ለእምላክ አብርሃም ዘአውዐአኒ ውስተ ፍኖተ ጽድቅ ከመ
እንሣእ ወለተ እኁሁ ለእግዚእየ ለወልዱ።

፵፱ ወይእዜኒ ለእመ ትገብሩ ምሕረተ ወጽድቀ ለእግዚ
እየ ንግሩኒ ወእመ አኮ አትመየጥ እመ አኮ የማነ ወእመ
አኮ ጸጋመ።
፶ ወአውሥእዎ በቱኤል ወላባ ወይቤልዎ እምኀበ እግ
ዚአብሔር ከነ ዝ ነገር ወኢንክል ተናግሮ ኢ ሠናየ ወኢ
እኩየ።
፶፩ ነያ ርብቃ ንሥኣ ወሑር ትኩን ብእሲተ ለወልደ እግ
ዚእከ በከመ ይቤሎ እግዚእከ።
፶፪ ወሰበ ሰምዐ ዘንተ ነገረ ሰገደ ዲበ ምድር።

፶፫ ወአውፅአ ውእቱ ገብር ሠርጐ ወርቅ ወብሩር ወአ
ልባሰ ሠናያተ ወወሀበ ለርብቃ፡ ወዓዲ ወሀበሙ አምኃ
ለአኀዊሃ ወለእማ።

፶፬ ወእምዝ በልዑ ወሰትዩ ውእቱኒ ወእለ ምስሌሁ ወቤ
ቱ፡ ወተንሥአ በጽባሕ ወይቤ፡ ፈንዉኒ ከመ እሑር ኀበ
እግዚእየ።
፶፭ ወይቤሉ እኁሃ ወእማ ወእኁሃ ትንበር ወለትነ ዐ
ሡረ መዋዕለ ምስሌነ ወእምዝ ተሐውር።
፶፮ ወይቤሎሙ ኢታስተጽንዑኒ፡ እንዘ እግዚአብሔር
ሠርሐኒ ፍኖትየ ፈንዉኒ ከመ እሑር ኀበ እግዚእየ።
፶፯ ወይቤልዎ ንጸውዓ ለርብቃ ወንስማዕ እምአፉሃ።

፶፰ ወጸውዕዋ ለርብቃ ወይቤልዋ ተሐውሪኑ ምስለ ዝ ብእሲ
ወትቤ እወ አሐውር።
፶፱ ወፈነውዋ ለርብቃ ምስለ ንዋይ ወለሐፃኒታ ወለገብረ
አብርሃምኒ ፈነውዎ ምስለ እሊአሁ።

፷ ወባረክዋ ለርብቃ እኅቶሙ ወይቤልዋ እኅትነ አንቲ
ኩኒ እልፈ ወአእላፈ አእላፋት ወይረስ ዘርእኪ አህጉረ
ፀር።
፷፩ ወተንሥአት ርብቃ ወሐፃኒታኒ ወተጽዕና አግማሊ
ሆን ወሖራ ምስለ ውእቱ ብእሲ፡ ወተወፈየ ውእቱ ብእሲ
ለርብቃ ወሖሩ።
፷፪ ወይስሐቅሰ ይዋሊ ውስተ ገዳም መንገለ ዐዘቅት ወሀ
ሰዉ ኅዱራን ውስተ ምድር እንተ መንገለ መስዕ።

፷፫ ወወፅአ ይስሐቅ ይዛዋዕ ውስተ ገዳም ፍና ሠርክ ወ
ሶበ ነጸረ ርእየ አግማለ እንዘ ይመጽኡ።

፷፬ ወሶበ ትኔጽር ርእየቶ ርብቃ ለይስሐቅ ወወረደት
እምላዕለ ገመል።
፷፭ ወተስእለቶ ለውእቱ ወልድ ወትቤሎ መኑ ውእቱ ዝ
ንቱ ብእሲ ዘያንሶሱ ውስተ ገዳም ወይትቄበለነ ወይቤላ
ዝንቱ ውእቱ እግዚእየ፡ ወነሥአት ሞጣሕታ ወተከድ
ነት ገጻ።

ዬን የወንድሙን ልጅ ለልጁ አመጣ ዘንድ ወደ እውነት
ጎዳና የመራኝን የጌታዬን የአብርሃምን ፈጣሪ አመሰገ
ንሁት። ዘፍ፡ ፳፬ ፳፯ - ፵፪። ፳፬ ፳፫። ፩ ነገ፡ ፷ ፳፯።
አሁንም ለጌታዬ እውነተኛ ቸርነትን ታደርጉ እንደ
ሆነ ንገሩኝ፤ ይህ ካልሆነ ግን ወደ ቀኝ ወደ ግራ ብዬ እፈ
ልጋለሁ አላቸው። ዘፍ፡ ፵፯ ፳፱። ኢያ፡ ፪ ፲፬።
በቱኤልና ላባም እንዲህ አሉት፤ ይህ ነገር ከእግዚአ
ብሔር ዘንድ ሁኗል፤ ክፉውንም ሆነ በጎ መናገር አንች
ልም። ዘፍ፡ ፴፩ ፳፬። ፪ ሳሙ፡ ፲፫ ፳፬።
ርብቃ ያቻትልህ ጌታህ እንዳዘዘህ ለጌታህ ልጅ ሚስት
ትሆነው ዘንድ ይዘሃት ሂድ። ዘፍ፡ ፲፫ ፲፬ - ፲፭።
ይህንም ነገር በሰማ ጊዜ በምድር ላይ ሰገደ።
ዘፍ፡ ፳፬ ፳፯ - ፵፰።
ያም አገልጋይ የብሩንና የወርቁን ጌጥ ያማረ ያማረው
ንም ልብስ አውጥቶ ለርብቃ ሰጣት፤ ዳግመኛም ለእናቷና
ለአባቷ እጅ መንሻ ሰጣቸው። ዘፀ፡ ፫ ፳፪። ፲፩ ፪። ፲፪
፴፭። ፪ ዜና መ፡ ፳፩ ፫። ዕዝ፡ ፩ ፯።
ከዚህ በኋላ እሱም ከሱ ጋራ ያሉትም በልተው ጠጥ
ተው አደሩ፤ በጧትም ተነሥቶ ወደ ጌታዬ ዘንድ ልሄድ
አሰናብቱኝ አላቸው። ዘፍ፡ ፳፬ ፩ - ፯። ፳፱ ፶፯ ፶፱።
እናቷና አባቷ ወንድሟም ልጃችን ፲ ቀን ከእኛ ጋራ
ትቀመጥ፤ ከዚህ በኋላ ትሄዳለች አሉት። ዘሌ፡ ፳፭ ፳፱።
እሱም እግዚአብሔር ጐዳናዬን አቅንቶልኝ ሳለ አትከለ
ክሉኝ ወደ ጌታዬም እሄድ ዘንድ አሰናብቱኝ አላቸው።
ርብቃን እንጥራትና የምትናገረውን ከአንደበቷ እን
ስማ አሉት።
ርብቃንም ጠርተው ከዚህ ሰው ጋራ ትሄጃን፤ አሏት
እሷም አዎን እሄዳለሁ አለች።
ርብቃንም ገንዘብ ሰጥተው ሰደዷት፤ ሞግዚቷንም
ጨምረው ሰደዷት፤ የአብርሃምንም መልእክተኛ ከወገ
ኖቹ ጋራ አሰናበቱት። ዘፍ፡ ፴፭ ፰።
እኅታቸው ርብቃንም አንቺ እኅታችን የብዙ ብዙ
ሁኚ፤ ዘርሽም የጠላቱን አገር ይግዛ ይውረስ ብለው መረ
ቋት። ዘፍ፡ ፲፯ ፲፯። ፳፪ ፲፯። ሩት፡ ፬ ፲፩።
ርብቃ ተነሣች ሞግዚቷም በግመሎቻቸው ተቀም
ጠው ከዚያ ሰው ጋራ ሄዱ፤ ያም ሰው ርብቃን ተረክ
ቧት ሄደ።
ይስሐቅ ግን በምድረ በዳ የራእይ ጕድጓድ በምትባ
ለው በኩል እያሸገረ ይመለከት ነበር፤ በዚያ በአዜብ
በኩል ባለችው ምድር ይኖር ነበርና። ዘፍ፡ ፲፯ ፲፬።
ይስሐቅም ሊዝናና ማታ ጊዜ ወደ ምድረ በዳ ወጣ፤
አንገቱንም ቀና አድርጎ በተመለከተ ጊዜ እነሆ ግመሎ
ችን ሲመጡ አየ። መዝ፡ ፶፫ ፲፯። ፸፯ ፯። ፻፲፱ ፲፭።
ርብቃም አሻግራ በተመለከተች ጊዜ ይስሐቅን አየ
ችው ከግመልም ላይ ወረደች። ኢያ፡ ፲፭ ፲፰።
እኛን ሊቀበለን በምድረ በዳ የሚዘዋወረው ይህ ሰው
ማነው፤ ብላ ያንን ብላቴና ጠየቀችው፤ እሱም ጌታዬ ይህ
ነው አላት፤ እሷም መጐናጸፊያዋን አንሥታ ፊቷን ተከ
ናነበች። ፩ ቆሮ፡ ፲፩ ፫ ፥ ፮ ፲።

| | | |
|---|---|---|
| ወዜነዎ ለይስሐቅ ውእቱ ወልድ ኵሉ ዘከመ ገብረ ። | ፷፮ | ያም ብላቴና ያደረገውን ሁሉ ለይስሐቅ ነገረው ። |
| ወበአ ይስሐቅ ውስተ ቤተ እሙ፤ ወነሥኣ ለርብቃ ወኮነቶ ብእሲተ ወአፍቀራ፤ ወአንገፍዎ ላሀ ለይስሐቅ በእንተ እሙ ። | ፷፯ | ይስሐቅም ወደ እናቱ ቤት ገባ ከዚህ በኋላ ርብቃን አገባት ሚስትም ሆነችው ወደዳትም፤ ይስሐቅንም ስለ እናቱ ሞት ልቅሶን አስተዉት ። ዘፍ፡ ፴፯ ፴፭ ። |
| ምዕራፍ ፳፭ ። | | ምዕራፍ ፳፭ ። |
| ወደገመ አብርሃም አውሰበ ብእሲተ እንተ ስማ ኬጡራ። | ፩ | አብርሃምም ስሟ ኬጡራ የምትባል ሚስትን ዳግመኛ አገባ ። |
| ወወለደት ሎቱ ወልደ ዘስሙ ዘንበሬ ወዮቃጤንሃ ወሚዶንሃ ወዮብቅሃ ወምድያምሃ ወሴሒሃ ። | ፪ | ስሙ ዘንበሬ የሚባል ልጅ ወለደች፤ ዮቃጤንን፤ ሜዶንን፤ ዮብቅን፤ ምድያምን፤ ሴሒን ወለደች ። ፩ ዜና መዋ፡ ፩ ፴፪ - ፴፫ ። |
| ወዮቃጤንሂ ወለዶሙ ለሰቤቅ ወለቴማን ወለዱዳን፤ ወዱዳን ወለዶሙ ለራጉኤል ወለንበብዘ ወለአስሬኢም ወለሎአም ። | ፫ | ዮቃጤንም ሰቤቅንና፤ ቴማንን፤ ዱዳንንም፤ ወለዳቸው፤ ዱዳንም እንቢብዘንና ራጉኤልን፤ ሎኢምንና አሴራኢምን ወለዳቸው ። |
| ወደቂቀ ምድያም ጌፌር ወኤፋር ወሄኖኅ ወአቤሮን ወቲያሬስ፤ እሉ ኵሎሙ ደቂቀ ኬጡራ ። | ፬ | የምድያምም ልጆች ጌፌር፤ ኤፋር ሄኖኅንና፤ አቤሮን፤ ቲያሬስም ናቸው፤ እሊህ ሁሉ የኬጡራ ልጆች ናቸው ። |
| ወወሀበ አብርሃም ኵሉ ንዋዮ ለይስሐቅ ወልዱ በሕይወቱ ። | ፭ | አብርሃምም ገንዘቡን ሁሉ ለልጁ ለይስሐቅ በሕይወቱ ሳለ ሰጠው ። ዘፍ፡ ፳፬ ፴፮ ። |
| ወለደቂቀ ዕቁባቲሁ ወሀበሙ አብርሃም ሀብተ ወፈነዎሙ እምገጸ ይስሐቅ ወልዱ ውስተ ምድር ዘመንገለ ምሥራቅ ። | ፮ | ለዕቍባቶቹ ልጆች ግን አብርሃም ፈንታ ፈንታቸውን ሰጥቶ ከልጁ ከይስሐቅ ፊት በምሥራቅ በኩል ወዳለች አገር አሰናበታቸው ። ዘፍ፡ ፳፩ ፲፬ ። መሳ፡ ፮ ፫ ። |
| ወዝንቱ ውእቱ ሕይወቱ ለአብርሃም ወዓመታቲሁኒ ምእት ወሰብዓ ወኀምስቱ ። | ፯ | የአብርሃም ዘመኑ ይህ ነው፤ ዕድሜውም ፻፸፭ ዓመት ነው ። |
| ወረሲዖ ጥቀ ሠናየ ርስዐ ወፈጺሞ መዋዕሊሁ ሞተ አብርሃም ወተወሰከ ኀበ ሕዝቡ ። | ፰ | አብርሃምም እጅግ በጎ እርጅናን አርጅቶ ዘመኑንም ጨርሶ ሞተ፤ ወደ ወገኖቹም ተጨመረ ። ዘፍ፡ ፲፭ ፲፭ ። |
| ወቀበርዎ ይስሐቅ ወይስማኤል ደቂቁ ውስተ በዐተ ክዕበት ዘገራህተ ኤፍሮን ዘሰዓር ኬጥያዊ ዘአንጻረ ምንባሬ ዘተሣየጠ አብርሃም እምደቂቀ ኬጢ ። | ፱ | ልጆቹ ይስሐቅና ይስማኤልም በወርቁ በገዛት በመምሬ ፊት ባለው ባለ ሁለት ክፍል የቀብር ቦታ አንፃር በምትገኘው በኬጥያዊው ሰዓር ልጅ በኤፍሮን እርሻ ባለችው ድርብ ዋሻ ቀበሩት። ዘፍ፡ ፱፡ ፲፫፡ |
| ወህየ ቀበርዎ ለአብርሃም፤ ወለሣራ ብእሲቱ ። | ፲ | አብርሃምን በዚያ ቀበሩት፤ ሚስቱን ሳራንም ። ዘፍ፡ ፳፫ ፲፯ ። ሥራ፡ ፯ ፲፮ ። መዝ፡ ፱ ፲፫ ። |
| ወኮነ እምድኅረ ሞተ አብርሃም ባረኮ እግዚአብሔር ለይስሐቅ ወልዱ ወኀደረ ይስሐቅ መንገለ ዐዘቅተ ራእይ። | ፲፩ | አብርሃምም ከሞተ በኋላ እንዲህ ሆነ፤ እግዚአብሔር ልጁን ይስሐቅን ባረከው፤ ይስሐቅም አብርሃም እግዚአብሔርን ባየበት ጕድጓድ አጠገብ ኖረ ። ዘፍ፡ ፲፯ ፲፱ ። |
| ወከመዝ ውእቱ ልደቱ ለይስማኤል ወልዱ ለአብርሃም ዘወለደት ሎቱ አጋር አመተ ሳራ ። | ፲፪ | የሳራ አገልጋይ አጋር የወለደችለት የአብርሃም ልጅ ይስማኤልም ትውልዱ እንዲህ ነው ። ዘፍ፡ ፲፯ ፲፩ ። |
| ወዝንቱ ውእቱ አስማቲሆሙ ለደቂቀ ይስማኤል በኵሩ ናቡአት ወቄዳር ወናብዳሄል ወመብሰን ። | ፲፫ | የይስማኤልም ልጆች ስማቸው ይህ ነው፤ የበኵር ልጁ ስሙ ናቡዓት ነው፤ ቄዳር፤ ናብዳሄል፤ መብሰን። ፩ ዜና መዋ፡ ፩ ፳፱ ። ፴ ፳፩ ። |
| ወማሴሜ ወዱማ ወማሴን። | ፲፬ | ማሴሜ፤ ዱማ፤ ማሴን ። |
| ወኩዳ ወቴማን ወኢያጤር ወናፌስ ወቄዳን ። | ፲፭ | ኩዳ፤ ቴማን፤ ኢያጤር፤ ናፌስ፤ ቄዳን ። ፩ ዜና ፩ ፴ ። |
| እሉ እሙንቱ ደቂቀ ይስማኤል ወዝንቱ ውእቱ አስማቲሆሙ፤ በበሀገሮሙ ወበበማኅበሮሙ ወበበብሔሮሙ ወበበሕዘቢሆሙ፤ ዐሠርቱ ወክልኤቱ መስፍንት ። | ፲፮ | የይስማኤል ልጆች እሊህ ናቸው፤ በየአገራቸው በየሸንጓቸው፤ በየመንደራቸው፤ በየወገናቸው የሚጠሩበት ስማቸው ይህ ነው፤ እነዚህም ፲፪ አለቆች ናቸው ። ዘፍ፡ ፲፯ ፳ ። |
| ወኀደረ እምኤዊሌዋ እስከ ሴይር እንተ ውስተ ግብጽ ወበጽሐ ውስተ አሶርዮን ወኀደረ ቅድመ ገጸ ኵሉ አኀዊሁ። | ፲፯ | ከኤዊሌዋ ጀምሮ በግብጽ እስካለች እስከ ሴይር ድረስ ተስፋፋ ወደ አሶርዮንም ደረሰ፤ በወንድሞቹም መካከል ኖረ ። ዘፍ፡ ፳፭ ፰ ። |
| ወዝንቱ ውእቱ ዓመተ ሕይወቱ ለይስማኤል ፻ወ፴ወ፯ | ፲፰ | ይስማኤል በሕይወት የኖረው ዘመን ፻፴፯ ዓመት ነው |

ዓመት፣ ወሞተ ረሲዖ ወተወሰከ ኀበ ሕዝቡ ።
፲፱ ወከመዝ ውእቱ ልደቱ ለይስሐቅ ወልደ አብርሃም ።

፳ አርበዓ ዓመቱ ለይስሐቅ አመ ነሥአ እማእከለ አፍላግ
ዘሶርያ ለርብቃ ወለተ በቱኤል ሶርያዊ እኅቱ ለላባ ከመ
ትኩኖ ብእሲተ ።
፳፩ ወሰአለ ይስሐቅ ኀበ እግዚአብሔር በእንተ ርብቃ
ብእሲቱ እስመ መካን ይእቲ ወሰምዖ እግዚአብሔር ወፀ
ንሰት ርብቃ ።
፳፪ ወይትሐወሱ ደቂቃ በውስተ ከርሣ ወትቤ እመሰ ሀለ
ወኒ እኩን ከመዝ ለምንት ሊተ ዝንቱ፣ ወሖረት ትሰአል
ኀበ እግዚአብሔር ።
፳፫ ወይቤላ እግዚአብሔር ክልኤቱ ሕዝብ ሀለዉ ውስተ
ከርሥኪ ወክልኤቱ ሕዝብ ይወፅኡ እምከርሥኪ፣ ወሕ
ዝብ እምሕዝብ ይኄይስ ወዘየዐቢ ይትቀነይ ለዘይንእስ ።
፳፬ ወተፈጸመ መዋዕለ ወሊዶታ ወክልኤቱ ሀለዉ
ውስተ ከርሣ ።
፳፭ ወወፅአ ወልዳ ዘበኵራ ወቀይሕ ኵለንታሁ ከመ ጽጌ
ረዳ ወጸጕር፣ ወሰመየቶ ስሞ ዔሳው፣ ወእምድኅሬሁ ወፅ
አ እኁሁ ወይእኅዝ በእዴሁ ሰኰና ዔሳው፣ ወበእንተዝ
ሰመየቶ ስሞ ያዕቆብ ።

፳፮ ወስሳ ዓመቱ ለይስሐቅ አመ ወለደቶሙ ርብቃ ለዔ
ሳው ወለያዕቆብ ።
፳፯ ወልህቁ ወኮኑ ወራዙተ ወኮነ ዔሳው ብእሴ ሐቅል
ነዓዌ፣ ወያዕቆብሰ ንጹሕ ውእቱ ወይነብር ውስተ ቤት ።

፳፰ ወያፈቅሮ ይስሐቅ ለዔሳው እስመ ዘውእቱ ነዓወ ይሴ
ሰይ፣ ወርብቃሰ ታፈቅሮ ለያዕቆብ ።
፳፱ ወአብሰለት ሎቱ ለያዕቆብ ተብሲለ ወመጽአ ዔሳው
እምሐቅል እንዘ ይደክም ።
፴ ወይቤሎ ዔሳው ለያዕቆብ፣ አብልዐኒ እምተብሲልከ
እስመ ደከምኩ ጥቀ ወበእንተ ዝንቱ ተሰምየ ስሙ ኤዶም ።
፴፩ ወይቤሎ ያዕቆብ ለዔሳው፣ አግብእኬ ሊተ ብኵርናከ ።
፴፪ ወይቤሎ ዔሳው፣ ናሁ እመውት ለምንት እንከ ሊተ
ከዊን በኵር ።
፴፫ ወይቤሎ ያዕቆብ፣ መሐልኬ ሊተ ዮም ከመ ታግብእ
ሊተ ብኵርናከ፣ ወመሐለ ሎቱ ዔሳው፣ ወአግብአ ሎቱ
ለያዕቆብ ከዊነ በኵር ።
፴፬ ወወሀበ ያዕቆብ ለዔሳው ኅብስተ ወተብሲለ ብርስን
ወበልዐ ወሰትየ፣ ወተንሥአ ወሖረ ።

ምዕራፍ ፳፮ ።

፩ ወኮነ ካልእ ረኃብ ውስተ ብሔር ዘእንበለ ረኃብ ዘኮነ
በመዋዕለ አብርሃም ወሖረ ይስሐቅ ኀበ አቤሜሌክ ንጉሠ
ፍልስጥኤም ውስተ ጌራራ ።
፪ ወአስተርአዮ እግዚአብሔር ወይቤሎ ኢትረድ ውስ
ተ ግብጽ ወኅድር ውስተ ምድር እንተ አነ እቤለከ ።

አርጅቶ ሞተ፣ ወደ ወገኖቹም ተጨመረ ። ዘፍ፣ ፲፮ ፯ ።
የአብርሃም ልጅ የይስሐቅ ትውልድም እንዲህ ነው ።
ማቴ፣ ፩ ፪ ።
ለይስሐቅም ሚስት ትሆነው ዘንድ የላባን እኅት የሶ
ርያዊውን ሰው የበቱኤልን ልጅ ርብቃን ከሶርያ ወን
ዞች መካከል በመጣት ጊዜ ፵ ዘመን ሆኖት ነበር ።
ይስሐቅም ስለ ሚስቱ ስለ ርብቃ ወደ እግዚአብሔር
ለመነ ሚስቱ መካን ነበረችና፣ እግዚአብሔርም ልመና
ውን ሰማው ርብቃም ፀነሰች ። ፩ ሳሙ፣ ፩ ፲፩ ።
ልጆቿም በማኅፀኗ ይራገጡ ነበር፣ እንዲህ የምሆን
ከሆነማ ይህ መውለድ ለምኔ ነው አለች፣ ትጠይቅም
ዘንድ ወደ እግዚአብሔር ሄደች ። ፩ ሳሙ፣ ፱ ፱ ።
እግዚአብሔርም ፪ት ሕዝብ በማኅፀንሽ አሉ፣ ፪ቱም
ሕዝብ ከማኅፀንሽ ይወጣሉ፣ ሕዝብ ከሕዝብ ይበልጣል፣
ታላቁም ለታናሹ ይገዛል አላት ። ዘፍ፣ ፲፯ ፲፯ ። ፳፬ ፰ ።
የምትወልድበት ወራት ደረሰ፣ ፪ት ልጆችም በማኅ
ፀኗ ነበሩ ።
የበኵር ልጅዋ ወጣ እንደ ጽጌረዳ ቀይ፣ ሁለንትና
ውም ጠጕር ነበር ስሙንም ኤሳው አለችው፣ ተከትሎ
ትም ወንድሙ ወጣ፣ የኤሳውንም ሰኰናውን በእጁ ጨ
ብጦ ነበር፣ ስለዚህም ስሙን ያዕቆብ አለችው ። ዘፍ፣ ፳፯
፲፩ ። ፲፯ ፳፫ ።
ርብቃ ያዕቆብና ኤሳውን በወለደቻቸው ጊዜ ለይስሐቅ
፷ ዓመት ሆኖት ነበር ። ዘፍ፣ ፳፯ ፴፯ ። ሆሴ ፲፪ ፫ ።
እነሱም አደጉ ጐለመሱም፣ ኤሳው በረኸኛ አዳኝ ሆነ፣
ያዕቆብ ግን ቅምጥል ነበር፣ ከቤትም አይወጣም ነበር ።
ዘፍ፣ ፳፯ ፫ - ፭ ። ፯ ፱ ። ኢዮብ ፩ ፩ - ፰ ። ፪ ፫ ።
ይስሐቅ ዔሳውን ይወድ ነበር እሱ ያደነውን ይመገብ
ነበርና፣ ርብቃ ግን ያዕቆብን ትወድ ነበር ። ዘፍ፣ ፳፯ ፬ - ፯ ።
ምስር ንፍሮም ቀቀለችለት ዔሳውም ከበረኻ ገባ ።

ዔሳውም ያዕቆብን እጅግ ደክሚያለሁና ከንፍሮህ አብ
ላኝ አለው፣ ስለዚህም ስሙ ኤዶም (ጉጉ) ተባለ ።
ያዕቆብም ዔሳውን ብኵርናህን ስጠኝ አለው ።
ዔሳውም እነሆ እኔ መሞቴ ነው፣ እንግዲህ በኵ
ርነት ምን ያደርግልኛል አለው ።
ያዕቆብም ብኵርናህን ልትሰጠኝ አሁን ማልልኝ አለ
ው፣ ዔሳውም ማለለት ብኵርናውንም ለያዕቆብ ሰጠው ።
ዕብ፣ ፲፪ ፲፯ ።
ያዕቆብም ለዔሳው ምስር ዳቦና ንፍሮ ሰጠው፣ በልቶ
ጠጥቶም ተነሥቶ ሄደ ።

ምዕራፍ ፳፮ ።

በአብርሃም ዘመን ከሆነው ረኀብ ሌላ በአገር ሁለተኛ
ረኀብ ሆነ፣ ይስሐቅም ከፍልስጥኤም ንጉሥ ከአቤሜሌክ
ዘንድ ወደ ጌራራ ሄደ ። ዘፍ፣ ፳ ፪ ። ፲፪ ፲ ። ፳፩ ፴፪ ።
እግዚአብሔርም ተገለጠለትና እንዲህ አለው ወደ ግብ
ጽ አትውረድ እኔ በፈቀድኩልህ ምድር ኑር ። ዘፍ፣ ፲፪ ፩ ።

| | | |
|---|---|---|
| ወንበር ውስተ ይእቲ ምድር ወእሐውር ምስሌከ ወእባርከከ፣ እስመ ለከ ወለዘርእከ እሁብ ለዛቲ ምድር፣ ወአቀውም ምስሌከ መሐላየ ዘመሐልኩ ለአብርሃም አቡከ ። | ፫ | በዚያችም አገር ተቀመጥ እኔም ከንተ ጋራ እኖራለሁ እባርክሃለሁ፣ ይህችን አገር ለአንተ ለልጆችህም እሰጣቻለሁና፣ ለአባትህ ለአብርሃም የማልኩለት መሐላዬንም ከአንተ ጋር አፀናለሁ ። ዘፍ፣ ፳ ፩ ። ዕብ፣ ፲፩ ፱ ። |
| ወአበዝኆ ለዘርእከ ከመ ከከበ ሰማይ፣ ወእሁብ ለዘርእከ ኵላ ዛተ ምድረ፣ ወይትባረኩ በዘርእከ ኵሉ አሕዛበ ምድር ። | ፬ | ዘርህንም እንደ ሰማይ ከከብ አበዛዋለሁ፣ ይህችንም አገር በሙላዋ ለልጆችህ እሰጣቻለሁ፣ የምድር አሕዛብ ሁሉ በዘርህ ይባረካሉ ። ዘፍ፣ ፲፪ ፫ ። |
| እስመ ሰምዐ አብርሃም ቃለ ዚአየ ወዐቀበ ትእዛዝየ ወኵነኔየ ወሕግየ ። | ፭ | አብርሃም ቃሌን እንደሰማ ትእዛዜን ፍርዴን ሕጌን እንደጠበቀ ። ዘፍ፣ ፳፪ ፲፮-፲፰ ። |
| ወነበረ ይስሐቅ ውስተ ጌራራ ። | ፮ | ይስሐቅም በጌራራ ኖረ ። |
| ወተስእልዎ ሰብአ ብሔር ለይስሐቅ በእንተ ርብቃ ብእሲቱ፣ ወይቤሎሙ እኅትየ ይእቲ፣ እስመ ፈርሀ አይድዮቶሙ ከመ ብእሲቱ ይእቲ ከመ ኢይቅትልዎ ሰብአ ውእቱ ብሔር በእንተ ርብቃ ብእሲቱ እስመ ሠናይ ገጻ ። | ፯ | የአገር ሰዎችም ይስሐቅን የሚስቱን የርብቃን ነገር ጠየቁት እሱም እኅቴ ናት አላቸው፣ ስለ ሚስቱ ስለ ርብቃ የዚያ አገር ሰዎች እንዳይገድሉት ሚስቴ ናት ብሎ መናገሩን ፈርቷልና መልከ መልክም ነበረችና ። ዘፍ፣ ፲፪ ፲፫ ። ፳፬ ፲፯ ። ምሳ፣ ፳፱ ፳፭ ። |
| ወነበረ ህየ ብዙኀ መዋዕለ ወሶበ ሐወጸ አቤሜሌክ እንተ መስኮት ርእዮ ለይስሐቅ እንዘ ይትዌነይ ምስለ ርብቃ ብእሲቱ ። | ፰ | በዚያም ብዙ ዘመን ኖረ፣ አቤሜሌክም በመስኮት በተመለከተ ጊዜ ይስሐቅን ከርብቃ ጋራ ሲጫወት አየው ። |
| ወጸውዖ አቤሜሌክ ለይስሐቅ ወይቤሎ ናሁ ብእሲትከ ይእቲ፣ ወትቤለኒ እኅትየ ይእቲ፣ ወይቤሎ ይስሐቅ፣ እስመ እቤ ይቀትሉኒ በእንቲአሃ ። | ፱ | አቤሜሌክም ይስሐቅን ጠርቶ እኅቴ ናት አልከኝ እንጂ እነሆ ሚስትህ ናት አለው፣ ይስሐቅም በእሷ ምክንያት ይገድሉኛል ብዬ ነው አለው ። |
| ወይቤሎ አቤሜሌክ፣ ምንትኑ ዝንቱ ዘረሰይከኒ ሕቀ ከመ ዘእምሰከበ ምስለ ብእሲትከ ብእሲ ዘእምአዝማድየ ወእምአምጻእከ ላዕሌየ ኃጢአተ በኢያእምሮ ። | ፲ | አቤሜሌክም ይህ ያደረግህብኝ ነገር ምንድር ነው፣ ከዘመዶቼ የሚሆን አንድ ሰው ከሚስትህ ሊተኛ ጥቂት ቀርቶት ነበር፣ ባለማወቅም ኃጢአት ታመጣብኝ ነበር ። ዘፍ፣ ፳፣ ፱ ። |
| ወአዘዘሙ ንጉሥ ለኵሎሙ ሕዘቢሁ፣ ወይቤሎሙ ኵሉ ዘለሐጠ ለዝንቱ ብእሲ ወለብእሲቱ ሞተ ለኩይ ኵነኔሁ ። | ፲፩ | ንጉሡም ይህን ሰው ሚስቱንም የነካ ሁሉ ፍርዱ ይሙት በቃ ነው ብሎ ሕዝቡን አዘዛቸው ። መዝ፣ ፻፭ ፲፭ ። |
| ወዘርአ ይስሐቅ ውስተ ይእቲ ምድር ወከነ ምእተ ምክዕቢተ፣ ወባረኮ እግዚአብሔር ። | ፲፪ | ይስሐቅም በዚያች ምድር ዘርን ዘራ፣ መቶ ዕዕፍም ሆነለት እግዚአብሔር ባረከው ። ማቴ፣ ፲፫ ፳፫ ። መዝ፣ ፻፲፪ ፫ ። |
| ወተለዐለ ወዐብየ ጥቀ ። | ፲፫ | ከፍ ከፍ አለ እጅግም ገነነ ። ምሳ፣ ፲ ፳፪ ። |
| ወአጥረየ አግብርተ ወእእማተ አባግዐ ወአልሕምተ ብዙኀ ወቀንኡ ላዕሌሁ ሰብአ ፍልስጥኤም ። | ፲፬ | ወንድ ባርያን ሴት ባርያን ላምን በግን አብዝቶ ገዛ፣ የፍልስጥኤም ሰዎችም ቀኑበት ። ዘፍ፣ ፴፯ ፲፩ ። መክ፣ ፬ ፬ ። |
| ወለኵሎሙ ዐዘቃት ዘከረዩ ደቀ አብርሃም በመዋዕለ አቡሁ ደፈንዎሙ ሰብአ ፍልስጥኤም ወመልእምሙ መሬተ ። | ፲፭ | በአባቱም ዘመን የአብርሃምን ብላቴኖች የቈፈሩዋቸውን ጕድጓዶች ሁሉ የፍልስጥኤም ሰዎች ደፈኑዋቸው፣ መሬትንም መሉዋቸው ። ዘፍ፣ ፳፩ ፴ ። |
| ወይቤሎ አቤሜሌክ ለይስሐቅ ሑር እምኔነ እስመ ጸናዕከነ ጥቀ ። | ፲፮ | አቤሜሌክም ይስሐቅን ፈጽመህ በርትተህብናልና ከኛ ተለይተህ ሂድ አለው ። |
| ወሖረ እምህየ ይስሐቅ ወኀደረ ውስተ ቈላተ ጌራራ ወነበረ ህየ ። | ፲፯ | ይስሐቅም ከዚያ ተነሥቶ በጌራራ ሸለቆ ሰፍሮ በዚያ ተቀመጠ ። ዘኁ፣ ፩ ፱ ። |
| ወካዕበ ከረዮን ይስሐቅ ለዐዘቃተ ማይ እለ ከረዩ አግብርተ አቡሁ አብርሃም ዘደፈንዎን ሰብአ ፍልስጥኤም እምድኅረ ሞተ አብርሃም አቡሁ፣ ወሰመዮን በበአስማቲሆን በከመ ሰመዮን አብርሃም ። | ፲፰ | ይስሐቅም ያባቱ የአብርሃም አገልጋዮች የቈፈሩዋቸው አባቱ አብርሃም ከሞተም በኋላ የፍልስጥኤም ሰዎች የደፈኑዋቸውን የውኃ ጕድጓዶች እንደገና ቈፈራቸው፣ አብርሃም እንደ ጠራቸውም በየስማቸው ጠራቸው ። |
| ወከረዩ አግብርተ ይስሐቅ ዐዘቅተ በቈላተ ጌራራ ወረከቡ ነቅዐ ማይ ጥዑመ ። | ፲፱ | የይስሐቅም አገልጋዮች በጌራራ ቈላ ጕድጓድ ቈፍረው የሚጣፍጥ የውኃ ምንጭ አገኙ ። |
| ወተባአሱ ኖሎተ ይስሐቅ ወኖሎተ ጌራራ ወይቤሉ ዚአነ ውእቱ ማይ፣ ወሰመያ ስማ ለይእቲ ዐዘቅት ዐዘ | ፳ | የይስሐቅ እረኞችና የጌራራ እረኞችም ይህ ውኃ የኛ ነው የኛ ነው በማለት ተጣሉ፣ ያችንም የወኃ ጕድ |

ቅተ ዐመፃ እስመ ዐመፅዎ ፡፡

፳፩ ወገዐዘ እምህየ ይስሐቅ ወከረየ ካልአተ ዐዘቅተ በህ የ ፡ ወተሳነንዎ በእንቲአሃ ወሰመያ ስማ ጽልእ ፡፡

፳፪ ወገዐዘ እምህየ ወከረየ ዐዘቅተ ፡ ወኢተበአስዎ በእን ቲአሁ ወሰመዮ ስሞ መርኅብ እንዘ ይብሉ እስመ አር ኀበ ለነ እግዚአብሔር ይእዜ ወአብዝኀነ ውስተ ምድር ፡፡

፳፫ ወገዐዘ እምህየ ኀበ ዐዘቅተ መሐላ ፡፡

፳፬ ወአስተርአዮ እግዚአብሔር በይእቲ ሌሊት ወይቤሎ ነየ አነ ውእቱ አምላኩ ለአብርሃም አቡከ ኢትፍራህ ሀለ ውኩ ምስሌከ ወእባርከከ ወአበዝኆ ለዘርእከ በእንተ አብርሃም አቡከ ፡፡

፳፭ ወነደቀ በህየ ምሥዋዐ ለእግዚአብሔር አምላኩ ወጸ ውዐ ስመ እግዚአብሔር ፡ ወተከለ በህየ ዐጸደ ወከረዩ በህየ ደቀ ይስሐቅ ዐዘቅተ ፡፡

፳፮ ወሐሩ ኀቤሁ እምነ ጌራራ አቤሜሌክ ወአኮዘት መጋ ቤ መራዕይሁ ወፋኮል መልአከ ሠራዊቱ ፡፡

፳፯ ወይቤሎሙ ይስሐቅ ለምንት መጻእክሙ ኀቤየ እም ድኅረ ጸላእክሙኒ ወአስቈረርክሙኒ ወሰደድክሙኒ እም ኀቤክሙ ፡፡

፳፰ ወይቤልዎ እስመ አኮ ንሕነ ዘአስቈረርናከ ፡ አላ አንበ ርናከ ሠናየ ወፈነውናከ በሠናይ ወይእዜኒ ቡሩክ አንተ ለእግዚአብሔር አምላክ ፡፡

፳፱ ወሰበ ርኢነ ከመ ሀሎ እግዚአብሔር አምላክ ምስሌከ ንቤ ከመ ይኩን ማእከሌከ ወማእከሌነ መሐላ ፡ ወንትማ ሐል ከመ ኢትግበር እኩየ ላዕሌነ ወኢንገበር እኩየ ላዕሌከ ፡፡

፴ ወገብረ ሎሙ ማእደ ወበልዑ ወሰትዩ ፡፡

፴፩ ወተንሥኡ ጽባሕ ወተማሐሉ በበይናቲሆሙ ፡ ወፈ ነዎሙ ይስሐቅ ወሐሩ በዳኅን ፡፡

፴፪ ወኮነ በይእቲ ዕለት በጽሑ አግብርቲሁ ለይስሐቅ ወነ ገርዎ በእንተ ዐዘቅት ዘከረዩ ወረከቡ ማየ በውስቴታ ፡፡

፴፫ ወሰመያ ስማ ቤርሳቤህ ፡ ወበእንተ ዝንቱ ተሰምየት ቤርሳቤህ ይእቲ ሀገር እስከ ዮም ፡፡

፴፬ ወኮኖ ለዔሳው አርብዓ ዓመተ ወነሥአ ብእሲተ እንተ ስማ ይድን ወለተ ቤኤል ኬጥያዊ ወቤሴሞት ወለተ ኤሎን ኤውያዊ ፡፡

፴፭ ወይትቃንዋሆሙ ለይስሐቅ ወለርብቃ ፡፡

## ምዕራፍ ፳፯ ፡፡

፩ ወኮነ እምድኅረ ልህቀ ይስሐቅ ወረስዐ ተሐምጋ አዕ ይንቲሁ ወኢይሬኢ ፡፡

፪ ወጸውዖ ለዔሳው ወልዱ ዘይልህቅ ወይቤሎ ናሁ ረሳ ዕኩ ወኢየአምር ዕለተ ሞትየ ፡፡

፫ ወይእዜኒ ንሣእ ንዋየ ሐቅልከ ወምጕንጳከ ወቀስትከ ወፃእ ሐቅለ ወነዐው ፡፡

ኀድ የዓመፅ-ጕድጓድ ብሎ ጠራት በምፀዉታልና ፡፡

ይስሐቅም ከዚያ ተጕዞ ሂዶ በዚያ ሌላ ጕድጓድ ቈፈረ ፡ በርሷም ምክንያት ተጣሉት ፡ ስሟንም ጠብ ብሎ ጠራት፡፡

ከዚያም ተጕዞ ሌላ ጕድጓድ ቈፈረ ፡ በርሱ ምክንያት ግን አልተጣሉትም ስሙንም ሰፊ አሉት ፡ ዛሬ እግዚአብ ሔር አሰፋልን በምድርም አበዛን አኮ ሲሉ ፡፡ ዘፀ፡ ፩ ፯ ፡፡

ከዚያም ተነሥቶ ወደ መሐላው ምንጭ ተጓዘ ፡፡

እግዚአብሔርም በዚያች ሌሊት ታየው ፡ የአባትህ የአ ብርሃም ፈጣሪ እኔ ነኝ አትፍራ ፡ እነሆ ከንተ ጋር አለሁና ስለ አባትህ ስለ አብርሃም ብየ አከብርሃለሁ ፡ ዘርህንም አበዛዋለሁ አለው ፡፡ ዘፍ፡ ፲፫.፩ ፡፡ ሮሜ ፰ ፴፩ ፡፡

በዚያም ለፈጣሪው ለእግዚአብሔር መሠውያን ሠራ ፡ የእግዚአብሔርንም ስም ጠራ ፡ በዚያም ድንኳን ተከለ ፡ የይስሐቅም ብላቴኖች ከዚያ የውኃን ጕድጓድ ቈፈሩ ፡፡ ዘፍ፡ ፲፫ ፲፰ ፡፡ መዝ፡ ፪፲፮ ፲፯ ፡፡

ንጉሡ አቤሜሌክ ላምራሱ አከዘትና የሠራዊቱ አለቃ ፋኮልም ከጌራራ ተነሥተው ወደርሱ ሄዱ ፡፡

ይስሐቅም ጠልታችሁኝ ተመቅኝታችሁኝ ከናንተ ለይ ታችሁ ከሰደዳችሁኝ በኋላ ለምን ወደኔ መጣችሁ ፤ አላ ቸው ፡፡ መሳ፡ ፲፩ ፯ ፡፡

እኛ የጠላንህ የተመቀኘንህ አይደለንም ፡ አክብረን አኑረን ደስ አሰኝተን ሸኝተን ሰደድንህ እንጂ አሉት አሁ ንም ለፈጣሪህ እግዚአብሔር የምትገዛ ቡሩክ ነህ ፡፡ ዘፍ፡ ፳፬ ፳፪-፳፫ ፡፡

ፈጣሪ እግዚአብሔር ከንተ ጋራ እንዳለ በየን ጊዜ በኛና በአንተ መከከል መሐላ ይደረግ እንላለን ፡ አሁንም አንተ በኛ ላይ ክፉ እንዳታደርግ እኛም በንተ ላይ ክፉ እንዳና ደርግ እንማማል አሉት ፡፡ ዘፍ፡ ፳፬ ፴፩ ፡፡መዝ፡ ፪፲፰ ፲፰ ፡፡

ማእድ አቅርበላቸው በሉም ጠጡም ፡፡ ዘፍ፡ ፲፱ ፫ ፡፡

ማልደውም ተነሥተው እርስ በርሳቸው ተማማሉ ፡ ይስሐቅ አሰናብቶአቸው በደኅና ሄዱ ፡፡ ዘፍ፡ ፳፩ ፴፩ ፡፡

በዚያች ሌሊት እንዲህ ሆነ ፡ የይስሐቅ አገልጋዮች ደርሰው የውኃ ጕድጓድ እንደቈፈሩና በውስጧም ውኃ እንዳገኙ ነገሩት ፡፡

ስምዋንም ቤርሳቤህ ብሎ ጠራት ፡ ስለዚህም ያች አገ ር ቤርሳቤህ ትባላለች ፡ እስከ ዛሬ ድረስ ፡፡

ለኤሳውም ፵ ዓመት ሲሆነው ስሟ ይድን የምትባል የኬጢያዊው የቤኤል ልጅንና የኤውያዊው ኤሎን ልጅ ቤሴሞትን አገባ ፡፡ ዘፍ፡ ፴፮ ፪ ፡፡

እነርሱም ይስሐቅንና ርብቃን ያሳዝኑዋቸው ነበር ፡፡ ዘፍ፡ ፳፯፡ ፵፮ ፡፡ ፳፰ ፩ ፡ ፰ ፡፡

## ምዕራፍ ፳፯ ፡፡

ይስሐቅ አርጅቶ ዓይኖቹ ፈዝዘው የማያይ ከሆነ በኋ ላ እንዲህ ሆነ ፡፡ ዘፍ፡ ፵፰ ፲ ፡፡ ፩ ሳሙ፡ ፫ ፪ ፡፡

ታላቁ ልጁ ኤሳውን ጠርቶ እነሆ አረጀሁ ዕለተ ሞቴ ንም አላውቅም ፡፡ ምሳ፡ ፳፯ ፩ ፡፡ ያዕ፡ ፬ ፲፬ ፡፡

አሁንም ማዳኛህንና አፎትህን ቀስትህንም ይዘህ በረኻ ሂደህ አድነህ ፡፡

፬ ወግበር ሊተ መብልዐ ዘከመ አፈቅር ወአምጽእ ሊተ እብላዕ ከመ ትባርከ ነፍስየ ዘእንበለ እሙት ።

ሳልሞት ነፍሴ እንድትመርቅህ እንደምወደው አድርገህ እበላ ዘንድ የምበላውን አምጣልኝ። ዘፍ፡ ፵፩ ፵፯-፵፰።

፭ ወሰምዐቶ ርብቃ ለይስሐቅ እንዘ ይብሎ ከመዝ ለዔሳው ወልዱ ፡ ወሖረ ዔሳው ሐቅለ ይንዐው ለአቡሁ ።

ርብቃም ይስሐቅ ለልጁ ለኤሳው እንዲህ ሲለው ሰማችው ኤሳውም ሊያድን በረኻ ሄደ ።

፮ ወትቤሎ ርብቃ ለያዕቆብ ወልዳ ዘይንእስ ፡ ናሁ አነ ሰማዕክዎ ለአቡከ እንዘ ይብሎ ለዔሳው እኁከ ።

ርብቃ ታናሹ ልጅዋ ያዕቆብን እንዲህ አለችው ፡ እነሆ አባትህ ወንድምህ ኤሳውን ።

፯ ሑር አምጽእ ሊተ እምዘነዐውከ ወግበር ሊተ መብልዐ ወእባርከ ቅድመ እግዚአብሔር ዘእንበለ እሙት ።

ሳልሞት በእግዚአብሔር ፊት እንድመርቅህ ከአደንከው አዘጋጅተህ የምበላውን አምጣልኝ ሲለው ሰምቼ ዋለሁ ።

፰ ወይእዜኒ ወልድየ ስምዐኒ ዘከመ እኤዝዘከ ።

አሁንም ልጄ ሆይ እሺ በለኝ በማዝህ ነገር ።

፱ ወሑር ኀበ አባግዒነ ወአምጽእ ሊተ ክልኤተ መሐስአ ሠናያነ ወእግበሮሙ መብልዐ ለአቡከ ዘከመ ያፈቅር።

ወደ በጎቻችን ሂደህ ያማሩ ሁለት ጠቦቶች አምጣልኝና አባትህ እንደሚወደው ምግብ አዘጋጃቸው ዘንድ ።

፲ ወትሰድ ለአቡከ ወይብላዕ ወይባርከ ዘእንበለ ይሙት።

ሳይሞት በልቶ እንዲመርቅህ ወስደህ ለአባትህ እንድትሰጠው አለችው ። ዘፍ፡ ፵፰ ፲፭ ።

፲፩ ወይቤላ ያዕቆብ ለርብቃ እሙ ናሁ ዔሳው እኁየ ጸጓር ውእቱ ወአንሰ ኢኮንኩ ጸጓረ ።

ያዕቆብም እናቱ ርብቃን እንዲህ አላት ፤ እነሆ ወንድሜ ኤሳው ጠጉራም ነው ፡ እኔ ግን ጠጉራም አይደለሁም ። ዘፍ፡ ፳፭ ፳፭ ።

፲፪ ወዮጊ እመ ገሠሠኒ አቡየ እከውን በቅድሜሁ ከመ ዘአስተሐቅሮ ወአመጽእ ላዕሌየ መርገመ ወአኮ በረከተ ።

ምናልባት አባቴ ቢዳስሰኝ በፊቱ እንደምዘብትበት እሆናለሁና ምረቃን ያይደለ በላዬ ላይ መርገምን አመጣለሁ። ዘፍ፡ ፱ ፳፭ ። ዘዳ፡ ፳፯ ፲፰ ።

፲፫ ወትቤሎ እሙ ላዕሌየ ይኩን መርገምከ ወልድየ ፡ ዳእሙ ስምዐኒ ወሑር ወአምጽእ ሊተ ዘእቤለከ ።

እናቱም ልጄ መርገምህ በኔ ላይ ይሁን ቃሌን ብቻ ስማኝ ፡ ሂድና የምልህን አምጣልኝ አለችው ። ዘፍ፡ ፵፫ ፱ ።

፲፬ ወሖረ ወአምጽአ ላቲ ለእሙ ወገብረት መብልዐ ዘከመ ያፈቅር አቡሁ ።

ሂዶም ለእናቱ አመጣላትና አባቱ እንደሚወደው አድርጋ መብሉን አዘጋጀች ።

፲፭ ወነሥአት ርብቃ አልባሲሁ ለዔሳው ወልዳ ዘይልህቅ ወዘይሤኒ ዘሀሎ ኀቤሃ ወአልበሰቶ ለያዕቆብ ወልዳ ዘይንእስ ።

ርብቃ ከርሷ ዘንድ የነበረ ያማረውን የታላቅ ልጅዋ የኤሳውን ልብስ አምጥታ ለታናሹ ልጅዋ ለያዕቆብ አለበሰችው ። ቊ፡ ፳፯ ።

፲፮ ወዝክተሂ እምአስቲሆሙ ለአልክቱ ክልኤቱ መሐስእ ወደየት ላዕለ መታክፍቲሁ ወላዕለ ክሳዱ ።

ያንን የሁለቱን ጠቦቶች ለምድ በትከሻውና በአንገቱ ላይ አደረገች ።

፲፯ ወወሀበቶ ዝኩ መብልዐ ወኅብስተኒ ዘገብረት በእደዊሁ ለያዕቆብ ወልዳ ።

ያን ያዘጋጀችውን እንጀራንና ጣፋጭ መብልን ለያዕቆብ በእጁ ሰጠችው ።

፲፰ ወአብአ ለአቡሁ ወይቤሎ አባ ፡ ወይቤሎ አቡሁ ነየ አነ ፡ መኑ አንተ ወልድየ ።

ወደ አባቱም ገብቶ አባቴ ሆይ! አለው ፡ አባቱም እነሆኝ ልጄ ሆይ አንተ ማነህ! አለው ።

፲፱ ወይቤሎ ያዕቆብ አነ ውእቱ ዔሳው ወልድከ ዘበኵርከ ገበርኩ ዘትቤለኒ ተንሥእ ወንበር ወብላዕ እምዘነዓውኩ ለከ ከመ ትባርከኒ ነፍስከ ።

ያዕቆብም እኔ የበኩር ልጅህ ዔሳው ነኝ ያልከኝን አድርጌ አለሁ ተነሥና ተቀመጥ ፡ ከአደንኩልህም ብላና ነፍስህ ትመርቀኝ ዘንድ አለው ።

፳ ወይቤሎ ይስሐቅ ለወልዱ ምንትኑ ውእቱ ዝንቱ ዘአፍጠንከ ረኪበ ወልድየ ፡ ወይቤሎ ዘወሀበኒ እግዚአብሔር አምላክከ ቅድሜየ ።

ይስሐቅም ለልጁ ልጄ ፈጥነህ ያገኘህ ይህ ምንድር ነው! አለው ፡ ፈጣሪህ እግዚአብሔር በፊቴ የሰጠኝ ነው አለው ።

፳፩ ወይቤሎ ይስሐቅ ቅረበኒ ወልድየ ወእገሥሥከ ለእመ አንተሁ ውእቱ ዔሳው ወለእመ ኢኮንከ ።

ይስሐቅም ልጄ! ቅረበኝ ልዳሥሥህ አንተ ዔሳው እንደሆንክ ወይም ያይደለህ እንደሆን አለው ።

፳፪ ወቀርበ ያዕቆብ ኀበ ይስሐቅ አቡሁ ወገሠሦ ወይቤሎ ቃልሰ ቃለ ያዕቆብ ወእደውሰ ዘዔሳው ።

ያዕቆብም ወደ አባቱ ወደ ይስሐቅ ቀረበ ፡ ዳሠሠውም ቃልህ የያዕቆብ ነው ፡ እጆችህ ግን የዔሳው ናቸው አለው።

፳፫ ወኢያእመሮ እስመ እደዊሁ ጸጓራት ከመ እደወ ዔሳው ፡ ወባረኮ ይስሐቅ ።

ነገር ግን አላወቀውም እጆቹ እንደ ዔሳው እጆች ጠጉራሞች ነበሩና ፡ ይስሐቅም መረቀው ። ቊ፡ ፲፮ ።

፳፬ ወይቤሎ አንተ ውእቱ ወልድየ ዔሳው ፡ ወይቤሎ ነየ አነ ።

አንተ ልጄ ዔሳው ነህን አለው ፡ እነሆ እኔ ልጅህ ነኝ አለው ። ሮሜ ፫ ፯-፰ ። ኤፌ፡ ፬ ፳፭ ።

፳፭ ወይቤሎ አምጽእ ሊተ እምዘነዐውከ ወልድየ ከመ እብላዕ ወትባርከ ነፍስየ ፡ ወአቅረበ ሎቱ ወበልዐ ወአም

ልጄ አድነህ ያመጣህልኝን በልቼ ሰውነቴ ትመርቅህ ዘንድ አምጣልኝ አለው ፡ አቅርቦለት በላም ወይንም አመ

| | | |
|---|---|---|
| ጽአ ሎቱ ወይነ ወሰትየ ። | | ጣለት ጠጣ ። |
| ወይቤሎ ይስሐቅ ቅረበኒ ወሰዐመኒ ወልድየ ። | ፳፮ | ይስሐቅም ልጄ ! ቀረብኝና ሳመኝ አለው ። |
| ወቀርበ ወሰዐሞ ወአጼነዎ ወጼነዎ ጼና አልባሲሁ ወይቤ ናሁ ጼናሁ ለወልድየ ከመ ጼና ገዳም ጥቀ ጥንቁቀ ዘባረከ እግዚአብሔር ። | ፳፯ | ቀርቦም ሳመው ፡ የልብሱንም ሽታ አሸተተው ፡ እነሆ የልጄ ልብስ ሽታው እግዚአብሔር እንደባረከው እንደ ዱር አበባ ሽታ ነው አለ ። |
| ወይቤሎ የሀብከ እግዚአብሔር እምጠለ ሰማይ ወእምጠለ ምድር ፡ ወያብዝኅ ሥርናየከ ወወይነከ ወቅብዐከ ። | ፳፰ | እግዚአብሔር ከሰማይ ጠል ፡ ከምድር ስብ ይሰጥህ ፡ ሥንዴህን ወይንህንና ዘይትህን ያብዛልህ አለው ። ሆሴ፡ ፲፬ ፯ ። መዝ፡ ፬ ፲፫ ። |
| ወይትቀነዩ ለከ አሕዛብ ወይስግዱ ለከ መላእክት ወኩን እግዚአ ለእኑከ ወይስግዱ ለከ ደቂቀ አቡከ ፡ ዘይባርከከ ቡሩከ ይኩን ፡ ወዘይረግመከ ርጉመ ለይኩን ። | ፳፱ | አሕዛብ ይገዙልህ ፡ አለቆችም ይስገዱልህ ፡ ለወንድሞችህም ጌታ ሁን ፡ የአባቶችህ ልጆች ይስገዱልህ አንተን የሚመርቅህ የተመረቀ ይሁን ፡ አንተን የሚረግምህም የተረገመ ይሁን ። |
| ወእምድኅረ እኅለቀ ባርኮቶ ይስሐቅ ለያዕቆብ ፡ ወዕአ ያዕቆብ እምቅድመ ገጸ ይስሐቅ አቡሁ ወመጽአ ዔሳው እምንዒው ። | ፴ | ይስሐቅ መርቆ ከጨረሰ በኋላ ያዕቆብ ከባቱ ከይስሐቅ ፊት ወጣ ፡ ዔሳውም ከአደን ተመልሶ መጣ ። |
| ወገብረ ውእቱሂ መብልዐ ወአምጽአ ለአቡሁ ወይቤሎ ተንሥእ አባ ወብላዕ እምዘነዐወ ለከ ወልድከ ከመ ትባርከኒ ነፍስከ ። | ፴፩ | እርሱም አድኖ ያመጣውን ምግብ አዘጋጅቶ ወደ አባቱ አመጣ ፡ አባቴ ሰውነትህ ትመርቀኝ ዘንድ እኔ ልጅህ አድኜ ከመጣሁት ተነሥተህ ብላ አለው ። |
| ወይቤሎ ይስሐቅ መኑ አንተ ፡ ወይቤሎ ዔሳው አነ ውእቱ ዔሳው ወልድከ ዘበኵርከ ። | ፴፪ | ይስሐቅም አንተ ማን ነህ አለው ፡ ዔሳውም እኔ የበኵር ልጅህ ዔሳው ነኝ አለው ። |
| ወደንገፀ ይስሐቅ ዐቢየ ድንጋፄ ጥቀ ወይቤሎ መኑመ ዘአምጽአ ሊተ ዘነዐወ ወበላዕኩ ወባረክዎ ወቡሩክ ውእቱ። | ፴፫ | ይስሐቅም እጅግ ደነገጠ ፡ ያደነውን ሠርቶ አዘጋጅቶ በልቼ የመረቅሁት ማን ነው ፤ እሱም የተባረከ ነው አለው ። ዘፍ፡ ፳፰ ፫ ፡ ፬ ። ኤፌ፡ ፩ ፫ ። |
| ወከነ ሶበ ሰምዐ ዔሳው ቃለ አቡሁ ጸርሐ በዐቢይ ቃል ወአምረረ ጥቀ ወይቤ ፡ ባርከኒ ኪያየኒ አባ ። | ፴፬ | ዔሳውም ያባቱን ነገር በሰማ ጊዜ በታላቅ ቃል ጮኸ ምርር ብሎም አለቀሰ ፡ አባቴ እኔንም መርቀኝ አለው ። |
| ወይቤሎ ይስሐቅ ለዔሳው መጽአ እኁከ በጕሕሉት ወነሥአ በረከተከ ። | ፴፭ | ይስሐቅም ወንድምህ በተንኰል መጥቶ በረከትህን ወሰደው አለው ። |
| ወይቤ ዔሳው በጽድቅ ተሰምየ ያዕቆብ እስመ አዕቀጸኒ ክልኤተ ጊዜ ፡ ቀዳሚ ብኵርናየ ነሥአኒ ወናሁ ዮምኒ በረከትየ ነሥአኒ ፡ ወይቤሎ ዔሳው አልቦኑ አባ ዘአትረፍከ ሊተ በረከተ ። | ፴፮ | ዔሳውም በእውነት ያዕቆብ ተባለ ሁለት ጊዜ አሰናክሎኛልና ፡ አስቀድሞ ብኵርናዬን ወሰደብኝ ፡ እነሆ ዳግመኛም በረከቴን ወሰደብኝ አለ ፡ ዔሳውም አባቴ ለእኔስ ያስቀረህልኝ በረከት የለምን ፤ አለው ። ዘፍ፡ ፳፭ ፳፯-፴፫ ። |
| ወአውሥአ ይስሐቅ ወይቤሎ ለዔሳው እግዚአከ ረሰይክዎ ወለኵሎሙ አኀዊሁ አግብርቲሁ ረሰይክዎሙ ወአብዛኅኩ ሎቱ ወይኖ ወሥርናዮ ወቅብዖ ፡ ወለከ ምንተ እሬሲ ወልድየ ። | ፴፯ | ይስሐቅም መልሶ ዔሳውን እንዲህ አለው ፤ ጌታህ አደረግሁት ወንድሞቹንም ሁሉ ተገዥዎቹ አደረግኋቸው ፡ ሥንዴውን ወይኑን ዘይቱን አበዛሁለት ፡ ልጄ ! ላንተስ ምን ላድርግልህ ፤ ፪ ሳሙ፡ ፰ ፲፬ ። ቍ፡ ፳፰ ። |
| ወይቤሎ ዔሳው ለይስሐቅ አቡሁ አሐቲኑ ከመ በረከትከ ለከሰ አባ ፡ ወአምዝ ጸርሐ ዔሳው ወበከየ ። | ፴፰ | ዔሳውም ይስሐቅን እንዲህ አለው ፤ አባቴ በረከትህ አንዲት ብቻ ናትን ፤ አባቴ እኔንም መርቀኝ እንጂ አለው ፡ ከዚህ በኋላ ድምፁን አሰምቶ አለቀሰ ። ዕብ፡ ፲፪ ፲፯ ። |
| ወይቤ ይስሐቅ ናሁ እምጠለ ሰማይ እምላዕሉ ወእምጠለ ምድር ይኩን ሕይወትከ ። | ፴፱ | ይስሐቅም እንዲህ አለ ፤ እነሆ መኖሪያህ ከምድር በላይ ካለ ከሰማይ በወረደ ጠል ከምድር በተገኘ ስብ ይሁን ። |
| ወበመጥባሕትከ ሕየው ወተቀነይ ለእኁከ ፡ ወባሕቱ እመ ትፈቅድ ትግድፍ ያሮ እምላዕለ ክሳድከ ተኃነይ ሎቱ ። | ፵ | በሰይፍህ አድነህ ኑር ፡ ለወንድምህም ተገዛ ፡ ነገር ግን አገዛዙን ከአንገትህ ሊቀልልህ ብትወድ ተለማመጥ ። |
| ወተበቀሎ ዔሳው ለያዕቆብ በእንተ በረከቱ ዘባረከ አቡሁ ፡ ወይቤ ዔሳው በልቡ ለትቅረብ መዋዕለ ላሁ ለአቡየ ከመ እቅትሎ ለያዕቆብ እኁየ ። | ፵፩ | ዔሳውም አባቱ ስለ መረቀው ምረቃ በያዕቆብ ቂም ያዘበት ፡ ዔሳው በልቡ ወንድሜ ያዕቆብን እገድለው ዘንድ የአባቴ የልቅሶው ቀን ትድረስ አለ ። |
| ወአይድዕዋ ለርብቃ ዘይቤ ወልዳ ዘይልህቅ ወለአከት ወጸውዐቶ ለያዕቆብ ወልዳ ዘይንእስ ፡ ወትቤሎ ናሁ ዔሳው እኁከ ይንዕወከ ወይፈቅድ ይቅትልከ ። | ፵፪ | ታላቁ ልጅዋ ዔሳው የተናገረውን ለርብቃ ነገሩዋት ፡ እሷም ታናሹ ልጅዋ ያዕቆብን ልካ አስጠርታ እነሆ ወንድምህ ዔሳው ያድንሃል ሊገድልህም ይፈልጋል ። |

፵፫ ወይእዜኒ ወልድየ ስምዐኒ ቃልየ ዘአነ እብለከ ተንሥእ ወሖር ማእከለ አፍላግ ዘሶርያ ኀበ ላባ እኁየ ውስተ ካራን።

አሁንም ልጄ የምልህን ነገር ስማኝ፤ ተነሥና በሶርያ ወንዞች መካከል ወዳለ ወደ ወንድሜ ላባ ወደ ካራን ሂድ አስቸው። ዘፍ፡ ፲፩ ፴፩።

፵፬ ወንበር ኀቤሁ ኅዳጠ መዋዕለ እስከ ይቀርር መዓቱ ለእኁከ።

የወንድምህ የቍጣው ቀን እስኪበርድለት ድረስ ጥቂት ቀን ከርሱ ዘንድ ተቀመጥ።

፵፭ ወይረስዕ ዘገበርከ ሎቱ ወእፌንወከ ወእነሥአከ እምህየ ከመ ኢይሕጐል ክልኤክሙ በአሐቲ ዕለት።

ያደረግኸውን ነገር እስኪረሳው ድረስ፤ ከዚያም ልኬ አስመጣሃለሁ፤ በአንድ ቀን ሁለታችሁን እንዳላጣ።

፵፮ ወትቤሎ ርብቃ ለይስሐቅ ጸላእኩ ሕይወትየ እምአዋልደ ከናአን ወእመሰ ይነሥእ ያዕቆብ ብእሲተ እምአዋልደ ዝንቱ ብሔር ለምንት እንከ አሐዩ።

ርብቃ ይስሐቅን እንዲህ አለችው፤ ከከነዓን ሴቶች (ከዔሳው ሚስቶች) የተነሣ ኑሮዬን ጠላሁ፤ ያዕቆብ ከዚህ አገር ልጆች ወገን ሚስት ያገባ እንደሆነ እንግዲህ በሕይወት መኖር ለምኔ ነው!። ዘፍ፡ ፳፮ ፴፭።

## ምዕራፍ ፳፰።

፩ ወጸውዖ ይስሐቅ ለያዕቆብ ወባረኮ፤ ወይቤሎ ኢትንሣእ ብእሲተ እምአዋልደ ከናአን።

ይስሐቅ ያዕቆብን ጠርቶ ባረከው፤ እንዲህም አለው፤ ከከነዓን ልጆች ወገን ሚስት አታግባ።

፪ ተንሥእ ወሖር ማእከለ አፍላግ ውስተ ቤተ ባቱኤል አቡሃ ለእምከ ወንሣእ ለከ ብእሲተ እምአዋልዲሁ ለላባ እኁሃ ለርብቃ እምከ።

ተነሥና በወንዞች መካከል ወዳለው ወደናትህ አባት ወደ ባቱኤል ቤት ሂደህ ከናትህ ርብቃ ወንድም ከላባ ልጆች ሚስት አግባ።

፫ ወአምላኪየ ይሖር ምስሌከ ወያዕቢከ ወይባርከ ወያብዝኅከ ወኩን ብዙኀ አሕዛበ።

ፈጣሪዬም ካንተ ጋር ይኑር፤ ያክብርህ፤ ይባርክህ ያብዛህ፤ ብዙ ሕዝብ ሁን።

፬ ወየሀብከ በረከተ አብርሃም አቡየ ለከ ወለዘርእከ እምድኅሬከ ከመ ትረስ ለይእቲ ምድር እንተ ወሀበ ለአብርሃም።

የአባቴ የአብርሃምን በረከት ላንተ ይስጥህ፤ ካንተም በኋላ ለዘርህ ለአብርሃም የሰጠው ይህችን ምድር ትወርሳት ዘንድ። ዘፍ፡ ፲፪ ፪።

፭ ወፈነዎ ይስሐቅ ለያዕቆብ ወሖረ ማእከለ አፍላግ ዘሶርያ ኀበ ላባ ወልደ ባቱኤል ሶርያዊ እኁሃ ለርብቃ።

ይስሐቅም ልጁ ያዕቆብን የርብቃ ወንድም የሶርያ ሰው የሚሆን የባቱኤል ልጅ ወዳለበት በሶርያ ወንዞች መካከል ወዳለው አገር አሰናበተው።

፮ ወሶበ ርእየ ዔሳው ከመ ባረኮ አቡሁ ለያዕቆብ ወከመ ሖረ ማእከለ አፍላግ ዘሶርያ ከመ ይንሣእ ብእሲተ እምህየ አመ ባረኮ ወከመ አዘዞ ወይቤሎ ኢትንሣእ ብእሲተ እምአዋልደ ከናአን።

ዔሳውም አባቱ ያዕቆብን እንደ መረቀው በየ ጊዜ በባረከውም ጊዜ ከዚያ ሚስት ያጭ ዘንድ በሶርያ ወንዞች መካከል ወዳለው አገር እንደሄደ በየ ጊዜ፤ ከከነዓንም ልጆች ወገን ሚስት አታግባ ብሎ እንደ አዘዘው በየ ጊዜ።

፯ ወሰምዖሙ ያዕቆብ ለአቡሁ ወለእሙ ወሖረ።

ያዕቆብም የአባቱንና የናቱን ሰምቶ ወደ ሶርያ እንደ ሄደ በየ ጊዜ።

፰ ወሶበ ርእየ ዔሳው ከመ እኩያት እማንቱ አዋልደ ከናአን በኀበ አቡሁ ይስሐቅ ሖረ ኀበ ይስማኤል።

ዔሳው የከነዓን ልጆች በአባቱ በይስሐቅ ዘንድ ክፉዎች እንደ ሆኑ በየ ጊዜ ወደ ይስማኤል ሄደ።

፱ ወነሥአ ለቤሴሞት ወለተ ይስማኤል ወልደ አብርሃም እኅቶ ለናኮር ከመ ትኩኖ ብእሲተ ምስለ አንስቲያሁ።

ከሚስቶቹ ጋር ሚስት ትሆነው ዘንድ የናኮር ወንድም የአብርሃም ልጅ የሚሆን የይስማኤል ልጅ ቤሴሞትን አገባ።

፲ ወወፅአ ያዕቆብ እምዐዘቅተ መሐላ ወሖረ ኀበ ካራን።

ያዕቆብም ከተማማሉበት የውኃ ጕድጓድ ወጥቶ ወደ ካራን ሄደ። ግብ፡ ሐዋ፡ ፯ ፪።

፲፩ ወረከበ መካነ ወቤተ ህየ፤ እስመ ዐርበት ፀሐይ ወነሥአ እምእብኑ እብነ ዘውስተ ውእቱ ብሔር ወወደየ ውስተ ትርአሲሁ ወሰከበ በውእቱ መካን።

ፀሐይ ገብቶ መሽቶ ነበርና ቦታ አግኝቶ ከዚያ አደረ፤ በቦታው ካለ ደንጊያ አንሥቶ ያንን ተንተርሶ በዚያ ቦታ ተኝቶ አደረ።

፲፪ ወሐለመ ወይሬኢ ሰዋስወ ዘወርቅ ውስተ ምድር ወርእሱ ይጐድእ ሰማየ፤ ወመላእክተ እግዚአብሔር የዐርጉ ወይወርዱ በቱ ወእግዚአብሔር ይቀውም ላዕሌሁ።

በዚያም ሌሊት በራእይ የወርቅ መሰላል ተተክሎ ከምድር እስከ ሰማይ ደርሶ አየ፤ መላእክትም ይወጡበት ይወርዱበት ነበር፤ በላዩም ላይ እግዚአብሔር ተቀምጦ አየ። ዘፍ፡ ፵፩ ፩።

፲፫ ወይቤሎ እግዚአብሔር አነ ውእቱ አምላከ አብርሃም ወአምላከ ይስሐቅ አቡከ፤ ኢትፍራህ ዛቲ ምድር እንተ ውስቴታ ትሰክብ ለከ እሁበከ ወለዘርእከ።

የአብርሃም ፈጣሪ የአባትህም የይስሐቅ ፈጣሪ እኔ እግዚአብሔር ነኝና አትፍራ አለው፤ የተኛህባትንም ምድር ላንተም ለልጆችህም እሰጣታለሁ። ዘፍ፡ ፲፫፡ ፲፮።

፲፬ ወይከውን ዘርእከ ከመ ኆፃ ባሕር ወይበዝኅ ወይመ

ዘርህም እንደ ባሕር አሸዋ ይሆናል፤ ይበዛል በአራት

ል እስከ ባሕር ወውስተ አዜብ ወመስዕ ፡ ወውስተ ጽባ
ሕ ወይትባረኩ ብከ ኵሎሙ አሕዛበ ምድር ወበዘርእከ ።
፲፭ ወናሁ አሐውር ምስሌከ ወአዐቅበከ በኵሉ ፍኖትከ
እንተ ትሐውር ወአገብአከ ውስተ ውእቱ ምድር ወኢየ
ኃድገከ እስከ እገብር ለከ ኵሉ ዘእቤለከ ።
፲፮ ወነቅሐ ያዕቆብ እምንዋሙ ወይቤ እግዚአብሔር ሀሎ
ውስተ ዛቲ ምድር ወአንሰ ኢያእመርኩ ።
፲፯ ወፈርሀ ወይቤ ግሩም ውእቱ ዝንቱ ምድር ወይከ
ውን ዝየ ቤተ እግዚአብሔር ወዛቲ ይእቲ ኆኅት ለሰማይ ።

፲፰ ወተንሥአ ያዕቆብ በጽባሕ ወነሥአ ለይእቲ እብን
እንተ ወደየ ውስተ ትርአሲሁ ወአቀማ ከመ ሐውልት
ወሦጠ ቅብዐ ላዕለ ርእሳ ።
፲፱ ወሰመየ ስሞ ለውእቱ መካን ቤተ ኤል ፡ ወስሙሰ
ሰውእቱ መካን ትካቲሁ ወለምሕሳ ።
፳ ወበፅዐ ያዕቆብ ወይቤ ለእመ ሀሎ እግዚአብሔር ምስ
ሌየ ወዐቀበኒ በዛቲ ፍኖት እንተ አሐውር ወወሀበኒ እክለ
ዘእበልዕ ወልብሰ ዘእለብስ ።
፳፩ ወአግብአኒ በዳኅን ቤተ አቡየ ይከውነኒ እግዚአብ
ሔር አምላኪየ ።

፳፪ ወዛቲ እብን እንተ አቀምኩ ትከውነኒ ቤተ እግዚአ
ብሔር ወኵሎ ዘወሀብከኒ ዓሥራተ እዴሁ እዔሥር ለከ ።

ምዕራፍ ፳፱ ።

፩ ወተንሥአ ያዕቆብ ወሖረ በጽባሕ ኀበ ላባ ወልደ ባቱ
ኤል ሶርያዊ እኁሃ ለርብቃ እሞሙ ለያዕቆብ ወለዔሳው ።

፪ ወሰበ ይኔጽር ወይሬኢ ናሁ ዐዘቅት ውስተ ገዳም ፡
ወሀለዋ ህየ ሠላሳ አባግዕ ወይሰክባ ላዕሌሃ ፡ እስመ እምነ
ይእቲ ዐዘቅት ያሰትይዎን ለውእቶን አባግዕ ወዓቢ እፉሃ
ለይእቲ ዐዘቅት እብን ዐቢይ ።
፫ ወይትጋብኡ ህየ ኵሎሙ ኖሎት ወያሴስልዋ ለይእቲ
እብን እምአፈ ዐዘቅት ወያሰትዩ አባግዒሆሙ ወያገብእዋ
ለይእቲ እብን ውስተ አፈ ዐዘቅት ።

፬ ወይቤሎሙ ያዕቆብ ፡ አንትሙ አኀውየ እምአይቴ
አንትሙ ፡ ወይቤልዎ እምነ ካራን ንሕነ ።
፭ ወይቤሎሙ ተአምርዎኑ ለላባ ወልደ ናኮር ፡ ወይቤ
ልዎ ነአምሮ ።
፮ ወይቤሎሙ ዳኅንኑ ውእቱ ፡ ወይቤልዎ እወ ዳኅን ፡
ወናሁ ራኄል ወለቱ ትመጽእ ምስለ አባግዐ አቡሃ ።
፯ ወይቤሎሙ ዓዲኑ ኢበጽሐ ሰዓት ከመ ይትጋብኡ
እንስሳከሙ ወይስተዩ ወይሑሩ ወይትረዐዩ ።
፰ ወይቤልዎ ኢንክል ለእመ ኢተጋብኡ ኵሎሙ ኖሎ
ት ፡ ወያሴስልዋ ለዛቲ እብን እምአፈ ዐዘቅት ወናሰቲ
አባግዒነ ።
፱ ወእንዘ ዘንተ ይትናገሩ በጽሐት ራኄል ምስለ አባ

መንግሥትን ሁሉ ይመላል ፡ በምድር ያሉ አሕዛብም ባንተም
በልጅህም ይከብራሉ ።
እኔም ካንተ ጋራ እሄዳለሁ ፡ በምትሄድበት መንገድ
ሁሉ እጠብቅሃለሁ ፡ ወደዚህም ምድር እመልስሃለሁ ያል
ኩህን ሁሉ እስክደርግልህ ድረስ አልለይህም ብሎ ነገረው ።
ያዕቆብም ከእንቅልፉ ነቅቶ እግዚአብሔር በዚህች
ምድር አለ እኔ ግን አላወቅሁም ነበር አለ ። ዘፀ፡ ፫ ፭ ።
ፈራ እንዲህም አለ ፤ ይህ ቦታ የሚያስፈራ ነው ፡ ከ
ዚህ ቤተ እግዚአብሔር ይሠራል የሰማይም ደጃፍ ይህ
ች ናት አለ ። ዮሐ፡ ፩ ፲፭ ።
ያዕቆብ ሲነጋ ተነሥቶ ትራስ ያደረጋትን ያችን ድን
ጊያ አንሥቶ እንደ ሐውልት አድርጎ አቆማት ፡ በላይዋም
ዘይት አፈሰሰባት ።
ያንንም ቦታ ስሙን ቤቴል ብሎ ጠራው ፡ የዚያ ቦታ
ጥንተ ስሙ ግን ወለምሕሳ ይባል ነበር ። መሳ፡ ፩፡ ፳፫ ።
ያዕቆብም እንዲህ ብሎ ተሳለ እግዚአብሔር ከእኔ ጋራ
ካለ በዚች በምሄድበትም መንገድ ከጠበቀኝ የምበላውን
እህል የምለብሰውን ልብስ ከሰጠኝ ።
ወዳባቴም ወገኖች በደኅና ከመለሰኝ ፡ ፈጣሪዬ እግ
ዚአብሔር የሚሰጠኝ ይህ ይበቃኛል ። መሳ፡ ፲፩ ፴፩ ።
፪ ሳሙ ፡ ፲፭ ፰ ።
ይህችም ያቆምኩዋት ድንጊያ የእግዚአብሔር ቤት
ትሆንልኛለች ፡ ከሰጠኸኝም ሁሉ "ካሥር አንድ„ አውጥቼ
ላንተ እሰጣለሁ ብሎ ተሳለ ። ዘፍ፡ ፴፭ ፯ ።

ምዕራፍ ፳፱ ።

ያዕቆብ ሲነጋ ተነሥቶ የያዕቆብና የዔሳው እናታቸው
የርብቃ ወንድም የሶርያ ሰው ከሚሆን ከባቱኤል ልጅ
ከላባ ዘንድ ሄደ ። ዘኍ፡ ፳፫ ፯ ። ሆሴ፡ ፲፪ ፲፪ ።
አሻግሮ በተመለከተ ጊዜ እነሆ በምድረ በዳ ያለውን
የውኃ ጕድጓድ አየ ፡ በዚያም ፴ በጎች ተኝተው ነበር ፡
እነዚያን በጎች ከዚያች የጕድጓድ ውኃ ያጠጡዋቸው ነበ
ርና በዚያችም ጕድጓድ አፍ ታላቅ ድንጊያ ተጋጥሞ ነበር ።
እረኞቹም ሁሉ ተሰብስበው ድንጊያውን ከምንጩ
አፍ አንሥተው በጎቻቸውን ያጠጡ ነበር ፡ በጎቻቸውንም
ካጠጡ በኋላ ድንጊያይቱን ከጕድጓዱ አፍ መልሰው ይገ
ጥሙዋት ነበር ።
ያዕቆብም እናንተ ወንድሞቼ ከወዴት ናችሁ ፤ አላ
ቸው ፡ ከወደ ካራን ነን አሉት ።
የናኮር ልጅ ላባን ታውቁታላችሁን ፤ አላቸው ፡ አዎን
እናውቀዋለን አሉት ።
ደኅና ነውን አላቸው ፡ አዎን ደኅና ነው አሁንም ልጁ
ራኄል ያባቷን በጎች ይዛ ትመጣለች አሉት ።
ከብቶቻችሁ ውኃ ለመጠጣት የሚሰበሰቡበት ጠጥ
ተውም የሚሠማሩበት ሰዓት አልደረሰምን አላቸው ።
እነሱም እረኞቹ ሁሉ ተሰብስበው ድንጊያዋን ከጕድ
ጓዱ አፍ ላይ ካላነሥዋት በጎቻችንን ለማጠጣት አንች
ልም አሉት ።
ይህንም ተናግረው ሳይጨርሱ ራኄል የአባቷን በጎች

ማሁ አቡሃ እስመ ይእቲ ትሬዒ አባግዐ ።
፲ ወሶበ ርእያ ያዕቆብ ለራሔል ወለተ ላባ እኍሁ ለእሙ
ሰዓማ ለራሔል ወጸርሐ በቃሉ ወበከየ ወአይድዓ ለራሔል
ከመ ወልደ ርብቃ እኅቱ ለአቡሃ ውእቱ ።

፲፩ ወአሰሰላ ለእብን እምአፈ ዐዘቅት ወአስተየ አባግዒሃ
ለራሔል ።
፲፪ ወሮጸት ራሔል ወሐረት ወአይድአቶ ለአቡሃ ዘንተ
ነገረ ።
፲፫ ወሶበ ሰምዐ ላባ ስመ ያዕቆብ ወልደ ርብቃ እኅቱ ሮጸ
ወተቀበሎ ወሐቀፎ ወሰዐሞ ወወሰዶ ቤቶ፤ ወነገሮ ለላባ
ኵሎ ነገሮ ።
፲፬ ወይቤሎ ላባ ለያዕቆብ ዐፅምየ ወሥጋየ አንተ ንበር
ምስሌየ፤ ወነበረ ምስሌሁ ሠላሰ መዋዕለ ።
፲፭ ወይቤሎ ላባ ለያዕቆብ እስመ እኍየ አንተ ኢትትቀ
ነይ ሊተ በከ፤ ንግረኒ ምንት ውእቱ ዐስብከ ።
፲፮ ወቦቱ ለላባ ክልኤቲ አዋልድ፤ ስማ ለአንቲ ትልህቅ
ልያ፤ ወለእንተ ትንእስ ራሔል ።
፲፯ ወልያሰ ትደዊ አዕይንቲሃ፤ ወለራሔልሰ ሠናይ ራእያ
ወላህይ ገጻ ።
፲፰ ወአፍቀራ ያዕቆብ ለራሔል፤ ወይቤሎ ያዕቆብ ለላባ
እትቀነይ ለከ ሰብዓተ ዓመተ በእንተ ራሔል ወለትከ እን
ተ ትንእስ ወሀበኒ ኪያሃ ከመ ትኩነኒ ብእሲተ ።
፲፱ ወይቤሎ ላባ ይኄይሰኒ ለከ እሁብከ ለማእምርየ ወለ
ሥጋየ እምአሀ፤ ለካልእ ብእሲ ነኪር፤ ንበር እንከሰ ።

፳ ወተቀንየ ያዕቆብ ሰብዓተ ዓመተ በእንተ ራሔል ወኮ
ኖ በቅድሜሁ ከመ ኅዳጥ መዋዕል እስመ አፍቀራ ።

፳፩ ወይቤሎ ያዕቆብ ለላባ ሀበኒ አንከሰ ብእሲትየ ከመ
እበእ ኀቤሃ እስመ ፈጸምኩ መዋዕሊሁ ።
፳፪ ወአስተጋብአሙ ላባ ለኵሎሙ ሰብአ ብሔሩ ወገብረ
ከብካበ ።
፳፫ ወሶበ መስየ ነሥአ ላባ ለልያ ወለቱ ወአብአ ኀበ
ያዕቆብ ።
፳፬ ወወሀበ ላባ ለልያ ወለቱ ዘለፋሃ ትኩና አመተ፤ ወሶበ
ጸብሐ ነያ ልያ ።
፳፭ ወይቤሎ ያዕቆብ ለላባ ለምንት ረሰይከኒ ከመዝ እኮኑ
በእንተ ራሔል ተቀነይኩ ለከ ወለምንት አስተሐቀርከኒ ።
፳፮ ወይቤሎ ላባ ኢኮነ ከመዝ በብሔርነ ኢይቀድሙ
ውሂበ እንተ ትንእስ እንዘ ሀለወት እንተ ትልህቅ ።
፳፯ ፈጽም ለዛቲኒ ሰብዓተ ዓመተ ወእሁበከ ኪያሃኒ በእ
ንተ ዘትትቀነይ ሊተ ካልእ ሰብዓተ ዓመተ ።
፳፰ ወገብረ ያዕቆብ ከማሁ ወፈጸመ ላቲኒ ሰብዓተ ዓመተ
ወወሀቦ ላባ ለያዕቆብ ራሔልሃ ።
፳፱ ወወሀባ ለራሔል ባላሃ ትኩና አመተ ።
፴ ወቦአ ያዕቆብ ኀበ ራሔል ወአፍቀራ ፈድፋደ እምልያ
ወተቀንየ ሎቱ ለላባ ካልአ ሰብዓተ ዓመተ በእንቲአሃ ።

ይዛ ደረሰች፤ እሷ በጎች ትጠብቅ ነበርና ።
ያዕቆብም የናቱ ወንድም የላባ ልጅ ራሔልን የላባን
በጎች ይዛ ስትመጣ ባየ ጊዜ ራሔልን ሳማት፤ ቃሉንም ከፍ
አድርጎ አለቀሰ፤ የአባቱ እኅት የርብቃ ልጅ መሆኑንም
ለራሔል ነገራት ።
ደንጊያይቱንም ከጕድጓዱ አፍ ላይ አንሥቶ የራሔ
ልን በጎች አጠጣ ። ዘፀ፣ ፪ ፲፯ ።
ራሔልም እየሮጠች ሄዳ ይህን ነገር ለአባቷ ነገረችው።

ላባም የእኅቱ የርብቃን ልጅ ስም በሰማ ጊዜ ፈጥኖ
ሂዶ አቅፎ ሰሞ ወደ ቤቱ ወሰደው፤ ያዕቆብ የመጣበት
ንም ሁሉ ነገር ለላባ ነገረው ።
ላባም ያዕቆብን አንተ አጥንቴ ሥጋዬ ነህና ከኔ ጋር
ተቀመጥ አለው፤ ከሱም ጋር ፴ ቀን ተቀመጠ፡ መሳ፣ ፱ ፪፡
ላባም ያዕቆብን አንተ ወንድሜ ነህና በከንቱ ለኔ አት
ገዛም ደመወዝህ ምን እንደሆነ ንገረኝ አለው ።
ለላባም ሁለት ሴቶች ልጆች ነበሩት፤ የትልቂቱ ስም
ልያ ነው፤ የትንሺቱም ስምዋ ራሔል ነው ።
ልያ ዓይነ ቃማሚ ነበረች፤ ራሔል ግን መልከ መል
ካም ነበረች፤ ፊቷም ውብ ነበር ።
ያዕቆብም ራሔልን ወደዳት፤ ያዕቆብ ስለ ትንሺቱ ል
ጅህ ፯ት ዓመት እገዛልሃለሁና ሚስት ትሆነኝ ዘንድ እሷን
ስጠኝ አለው ። ዘፍ፣ ፴፩ ፵፩ ።
ላባም ለሌላ ባዕድ ሰው ከምሰጣት ይልቅ ለማውቅህ
ላንተ ለዘመዴ ብሰጣት ይሻለኛል እንግዲያውስ ተቀመጥ
አለው ።
ያዕቆብም ስለ ራሔል ፯ት ዓመት ተገዛ፤ ራሔልን ስለ
ወደዳት ፯ቱ ዓመት ለያዕቆብ እንደ ጥቂት ቀን ሆነለት ።
ዘፍ፣ ፴ ፳፮ ። መኃ፣ ፰ ፯ ።
ያዕቆብም ለላባ ዘመኑን ፈጽሜ አለሁና እንግዲህስ
እገናኛት ዘንድ ሚስቴን ስጠኝ አለው ። መሳ፣ ፲፭ ፩ ።
ላባም የአገሩን ሰዎች ሁሉ ሰብስቦ ሠርግ አደረገ ።

በመሸም ጊዜ ላባ ልጁ ልያን ወስዶ ለያዕቆብ አገባለት።

ላባም ለልጁ ልያ አገልጋይ ትሆናት ዘንድ ዘለፋን
ሰጣት፤ ሲነጋም እነሆ ልያ ሆና ተገኘች ።
ያዕቆብም ላባን ለምን እንዲህ አደረግህብኝ ያገለገል
ሁህ ስለ ራሔል አልነበረምን ለምንስ አታለልከኝ አለው ።
ላባም ነገሩ እንዲህ አይደለም፤ በአገራችን ታላቂቱ
ሳለች ትንሺቱን አይድሩም አለው ።
ለዚችም ፯ቱን ዓመት ፈጽምና እርሷንም እሰጥሃለሁ
ሁለተኛ ሰባት ዓመት የምትገዛልኝ ስለሆነ አለው ።
ያዕቆብም እንዲህ አደረገ ለርሷም ፯ት ዓመት ተገዛ
ለት፤ ላባም ለያዕቆብ ራሔልን ሰጠው ።
ላባ ለራሔል አገልጋይ ትሆናት ዘንድ ባላን ሰጣት ።
ያዕቆብም ወደ ራሔል ገባ፤ ከልያም ይልቅ ፈጽሞ
ወደዳት፤ ያዕቆብ ራሔልን ካገባም በኋላ ዳግመኛ ስለርሷ
፯ት ዓመት አገለገለው ። ሆሴ፣ ፲፪ ፲፪ ።

፴፩ ወሶበ ርእየ እግዚአብሔር ከመ ትጸልእ ልያ ፈትሐ ማኅፀና፤ ወራሔልሰ ከነት መካነ ።

እግዚአብሔር ልያ በያዕቆብ ዘንድ እንደ ተጠላች ባየ ጊዜ ማኅፀኗን ከፈተላት፤ ራሔል ግን መካን ሆነች ።

፴፪ ወፀንሰት ልያ ወወለደት ወልደ ወሰመየቶ ስሞ ሮቤል እንዘ ትብል እስመ ርእየ እግዚአብሔር ትሕትናየ፤ ወእምይእዜሰ ያፈቅረኒ ምትየ ።

ልያም ፀንሳ ወንድ ልጅ ወለደች፤ ስሙንም ሮቤል አለችው፤ እግዚአብሔር መዋረዴን ስላየ ከእንግዲህስ ወዲህ ባሌ ይወደኛል ስትል ። ዘዐ፣ ፫ ፯ ። ዘዳ፣ ፳፮ ፯ ።

፴፫ ወዳግመ ፀንሰት ልያ ወወለደት ካልአ ወልደ ለያዕቆብ ወትቤ እስመ ሰምዐኒ እግዚአብሔር በእለትየ ከመ እጸልእ ወሰከኒ ዘንተ፤ ወሰመየቶ ስሞ ስምዖን ።

ዳግመኛም ልያ ፀንሳ ለያዕቆብ ሌላ ወንድ ልጅ ወለደችለት፤ እግዚአብሔር እንደ ተጠላሁ አይቶ ልመናዬንም ሰምቶ ይህን ጨመረልኝ ስትል ስሙን ስምዖን አለችው ።

፴፬ ወፀንሰት ዓዲ ወወለደት ወልደ ወትቤ እምይእዜሰ ኀቤየ ውእቱ ምትየ እስመ ወለድኩ ሎቱ ሠለስተ ደቂቀ፤ ወሰመየቶ ስሞ ሌዊ ።

ሦስተኛም ፀንሳ ወንድ ልጅ ወለደች፤ ሦስት ልጆች ወልጄለታለሁና እንግዲህስ ወዲህ ባሌ ወዳጄ ነው ስትል ስሙን ሌዊ አለችው ።

፴፭ ወፀንሰት ዓዲ ወወለደት ወልደ ወትቤ ይእዜ በእንተዝ እአምኖ ለእግዚአብሔር አምላክ፤ ወበእንተዝ ሰመየቶ ስሞ ይሁዳ፤ ወአቀመት ወሊደ ።

ደግሞም ፀንሳ ወንድ ልጅ ወለደች፤ አራተኛ ልጅ ሰጥቶኛልና ስለዚህ ፈጣሪዬ እግዚአብሔርን አምነዋለሁ ስትል ስሙን ይሁዳ አለችው፤ ከዚህ በኋላ መውለድን አቋረጠች ።

## ምዕራፍ ፴ ።

፩ ወሶበ ርእየት ራሔል ከመ ኢወለደት ለያዕቆብ ቀንአት ላዕለ ልያ እኅታ ወትቤሎ ለያዕቆብ ሀበኒ ወልደ ወእመ አኮ እመውት ።

ራሔል ለያዕቆብ ልጅ እንዳልወለደችለት በየች ጊዜ በእኅቷ በልያ ላይ ቀናች፤ ያዕቆብንም ወንድ ልጅ ስጠኝ አለበለዚያ እሞታለሁ አለችው ። ኢዮብ ፭ ፪ ።

፪ ወተምዓ ያዕቆብ ለራሔል ወይቤላ ከመ እግዚአብሔርኑ አነ ዘአከልአኪ ፍሬ ከርሥኪ ።

ያዕቆብም የማኅፀንሽን ፍሬ የምነሣሽ እኔ እንደ እግዚአብሔር ነኝን ብሎ ራሔልን ተቈጣት ። ፩ ሳሙ፣ ፩ ፭ ።

፫ ወትቤሎ ራሔል ነያ አመትየ ባላ ሑር ባእ ኀቤሃ ወትለድ ዲበ አብራክየ ወእትዋለድ አነኒ እምኔሃ፤ ወወሀበቶ ባላሃ ትኩኖ ብእሲተ ።

ራሔልም ያዕቆብን እንዲህ አለችው፤ እነሆ አገልጋዬ ባላ አለች፤ ድረስባት በኔ ጭን ላይ ትውለድ፤ እኔም ከርሷ በተወለደው ልጅ እዛመዳለሁ ብላ ሚስት ትሆነው ዘንድ ባላን ሰጠችው ። ዘፍ፣ ፲፮ ፪ ።

፬ ወበአ ያዕቆብ ኀቤሃ ወፀንሰት ባላ ወወለደት ወልደ ለያዕቆብ ።

ያዕቆብም ባላን ቢደርስባት ፀንሳ ለያዕቆብ ወንድ ልጅ ወለደችለት ።

፭ ወትቤ ራሔል ፈትሐ ሊተ እግዚአብሔር ወሰምዐኒ ቃልየ ወወሀበኒ ወልደ፤ ወበእንተዝ ሰመየቶ ስሞ ዳን ።

ራሔልም እግዚአብሔር ፈረደልኝ፤ ልመናዬንም ሰምቶ ወንድ ልጅ ሰጠኝ አለች፤ ስለዚህም ስሙን ዳን አለችው ። መዝ፣ ፵፫ ፩ ።

፮ ወፀንሰት ዓዲ ባላ አመተ ራሔል ወወለደት ካልአ ወልደ ለያዕቆብ ።

የራሔል ገረድ ባላም ፀንሳ ለያዕቆብ ሁለተኛ ወንድ ልጅ ወለደችለት ።

፯ ወትቤ መጠቀኒ እግዚአብሔር ወመሰልክዋ ለእኅትየ ወኀየልክዋ፤ ወሰመየቶ ስሞ ንፍታሌም ።

እግዚአብሔርም ክፍ ክፍ አደረገኝ እኅቴንም ተበራትቼ መሰልኋት ስትል ስሙን ንፍታሌም አለችው ። ማቴ፣ ፬ ፲፫ ።

፰ ወሶበ ርእየት ልያ ከመ ኢወለደት ወኀደገት ወሊደ ነሥአታ ለዘለፋ አመታ ወወሀበቶ ለያዕቆብ ትኩኖ ብእሲተ ።

ልያም እንዳልወለደች መውለድንም እንዳቆመች በየች ጊዜ፤ አገልጋይዋ ዘለፋን ወስዳ ሚስት ትሆነው ዘንድ ለያዕቆብ ሰጠችው ።

፱ ወፀንሰት ዘለፋ ለያዕቆብ ወወለደት ወልደ ።

ዘለፋም ፀንሳ ለያዕቆብ ወንድ ልጅ ወለደች ።

፲ ወትቤ ልያ አብፃዕኩ አነኒ፤ ወሰመየቶ ስሞ ጋድ ።

ልያም እኔም ብፅዕት ተባልኩ ስትል ስሙን ጋድ አለችው ።

፲፩ ወፀንሰት ዓዲ ዘለፋ ወወለደት ለያዕቆብ ።

ዳግመኛም ዘለፋ ፀነሰች፤ ለያዕቆብም ወንድ ልጅ ወለደች ።

፲፪ ወትቤ ልያ ብፅዕት አነ ወያስተበፅዓኒ አንስት፤ ወሰመየቶ ስሞ አሴር ።

ልያ እኔ ንእድት ክብርት ነኝ፤ ሴቶችም ያከብሩኛል ስትል ስሙን አሴር አለችው ። ምሳ፣ ፴፩ ፳፰። ሉቃ፣ ፩ ፵፰።

፲፫ ወሖረ ሮቤል በመዋዕለ ማእረረ ሥርናይ ወረከበ ኮለ በሐቅል ወአምጽአ ላቲ ለእሙ፤ ወትቤላ ራሔል ለልያ ሀብኒ ኮለ ዘወልድኪ ።

ሮቤልም የሥንዴ አዝመራ በሚታጨድበት ወራት ሄዶ ከበረሃ እንኮይን አግኝቶ ለናቱ አመጣላት፤ ራሔልም ልያን የልጅሽን እንኮይ ስጪኝ አለቻት ። ዘፍ፣ ፳፭ ፴።

፲፬ ወትቤላ ልያ ኢአከለኪኑ ዘነሣእክኒ ምትየ ዓዲ ትፈ

ልያም ራሔልን ባሌ የወሰድሽብኝ አልበቃሽምን ደግ

ቅዱ ትንሥእኒ ክለሂ ዘወልድየ ወትቤላ ራኄል ለልያ አከ
ከማሁ ለይቢት ዮም ኅቤኪ በእንተ ከል ዘወልድኪ
ወወሀበታ ።

፲፭ ወአተወ ያዕቆብ እምሐቅል ፍና ሠርክ ወተቀበለቶ
ልያ ፍና ሠርክ ወትቤሎ ኅቤየ ትበይት ዮም እስመ ተሣ
የጥኩከ በከል ዘወልድየ ፡ ወቤተ ኅቤሃ በይእቲ ሌሊት ።
፲፮ ወሰምዓ እግዚአብሔር ለልያ ወፀንሰት ወወለደት
ወልደ ኃምሰ ።
፲፯ ወትቤ ልያ ወሀበኒ እግዚአብሔር ዐስብየ እስመ ወሀ
ብክዋ ከለ ሐቅል ዘወልድየ ፡ ወሰየመቶ ስሞ ይሳኮር ፡
ዐስብ ብሂል ።
፲፰ ወፀንሰት ዳዲ ልያ ወወለደት ወልደ ሳድሰ ለያዕቆብ።

፲፱ ወትቤ ልያ ፈትሐ ሊተ እግዚአብሔር ሠናየ ፍትሐ
እምዮምሰ እንከ ያፈቅረኒ ምትየ እስመ ወለድኩ ሎቱ
ስድስተ ደቂቀ ፡ ወሰመየቶ ስሞ ዛብሎን ።
፳ ወእምዝ ወለደት ወለተ ወሰመየታ ስማ ዲና ።

፳፩ ወተዘከራ እግዚአብሔር ለራኄል ወፈትሐ ማኅፀና ።

፳፪ ወፀንሰት ወወለደት ወልደ ለያዕቆብ ወትቤ አውዕአ
እግዚአብሔር እምላዕሌየ ዝንጓጔየ ።
፳፫ ወሰመየቶ ስሞ ዮሴፍ ፡ ወትቤ ይወስከኒ እግዚአብ
ሔር ወልደ ካ.ለ ።
፳፬ ወሶበ ወለደት ራኄል ዮሴፍሃ ይቤሎ ያዕቆብ ለላባ
ፈንወኒ ከመ እሑር ብሔርየ ወውስተ ምድርየ ።
፳፭ ወሀበኒ ደቂቅየ ወአንስቲያየ ዘበእንቲአሆን ተቀነይኩ
ለከ ወለሊከ ተአምር ዘከመ ተቀነይኩ ለከ ።
፳፮ ወይቤሎ ላባ ለእመ ረከብኩ ሞገሰ በቅድሜከ እስመ
አእመርኩ ከመ ባረከኒ እግዚአብሔር በእንቲአከ ።
፳፯ ፍልጥ ሊተ ዐስበከ ዘእሁበከ ።
፳፰ ወይቤሎ ያዕቆብ ኢ.ተአምርኑ ከመ ተቀነይኩ ለከ ፡
ወሚመጠን እማንቱ እንስሳከ ዘኅቤየ ።
፳፱ እስመ ረከብክምን ኅዳጣተ ወመልአ ወበዝኃ ወባረከን
እግዚአብሔር በእግረ ዚአየ ፡ ወይእዜኒ ማእዜኑመ እገብር
አንሰ ቤተ ለርእስየ ።
፴ ወይቤሎ ላባ ምንተኑመ አሁብከ ፡ ወይቤሎ ያዕቆብ
አልቦ ዘትሁበኒ ወኢ.ምንተኒ ፡ ለእመ ገበርከ ሊተ ዘንተ
ነገረ እርዒ ክዕበ አባግዒከ ወአዐቅብ ።

፴፩ ወይኅልፉ ኵሎን አባግዒከ ዮም ወፍልጥ ሊተ እም
ውስቴቶን ኵሎ በግዐ ዘፀዐዳ ጸጕሩ ወዘኰሳኵስ ኅብሩ
ወፍጥረቱ ይኩነኒ ዐስብየ ።
፴፪ ወኵሉ ዘኢ.ኮነ ኰሳኵሰ ወዘኢ.ኮነ ፀዐዳ ፍጥረቱ ለከ
ይኩንከ ውእቱ ።
፴፫ ወይቤሎ ላባ ይኩን በከመ ትቤ ።
፴፬ ወፈለጠ በይእቲ ዕለት አብሐኰ አባግዐ ዘኰሳኵስ
ወዘፀዐዳ ወኵሎ አብሐኰ አጣሊ ዘኰሳኵስ ወዘፀዐዳ ወዘ

ም ልጄ ያመጣውን እንኮይ ልትወስጂብኝ ትፈልጊያለሽን
አለቻት ፡ ራኄልም ልያን እንዲህ አይደለም ልጅሽ ያመጣ
ውን እንኮይ ስለ ሰጠሽኝ ዛሬ ከንቺ ጋር ይደር ብላ
ሰጠቻት ። ዘኍ፡ ፲፯ ፱ ።
ያዕቆብም ሲመሽ ከበረኻ ገባ ፡ ልያም ማታ ሲመጣ
ተቀበለችው ፡ በልጄ እንኮይ ገዝቼኻለሁና ዛሬ ከኔ ጋር
ታድራለህ አለችው ፡ በዚያችም ሌሊት ከርሷ ጋር አደረ።
እግዚአብሔር የልያን ልመና ሰምቶ ፀንሳ አምስተኛ
ወንድ ልጅ ወለደች ።
ልያም ልጄ ያመጣውን የበረኻ እንኮይ ስለ ሰጠኋት
እግዚአብሔር ዋጋዬን ሰጠኝ አለች ፡ ስሙንም ይሳኮር
አለችው ።
ልያም ዳግመኛ ፀንሳ ለያዕቆብ ስድስተኛ ወንድ ልጅ
ወለደችለት ።
ልያም እግዚአብሔር መልካም ፍርድ ፈረደልኝ ስድ
ስት ልጆች ስለ ወለድኩለት እንግዲህስ ወዲህ ባሌ ይወ
ደኛል ስትል ስሙን ዛብሎን አለችው ።
ከዚህ በኋላ ሴት ልጅ ወለደች ስሟንም ዲና ብላ
ጠራቻት ።
እግዚአብሔርም ራኄልን አሰበት ማኅፀኗንም ከፈተ
ላት ። ፩ ሳሙ፡ ፩ ፲፱ ። ዘፍ፡ ፳፱ ፴፩ ።
ፀንሳም ለያዕቆብ ወንድ ልጅ ወለደችለት ፡ እግዚአብ
ሔርም ስድቤን አስወገደልኝ አለች ።
ስሙንም ዮሴፍ አለችው ፡ እግዚአብሔር ሁለተኛ
ወንድ ልጅ ይጨምርልኝ ስትል ። ዘፍ፡ ፴፭ ፲፯ ።
ራኄል ዮሴፍን በወለደች ጊዜ ያዕቆብ ላባን ወደ
አገሬ ወደ ርስቴ እመለስ ዘንድ አሰናብተኝ አለው ።
ስለ እርሳቸው የተገዛሁልህ ልጆቼንና ሚስቶቼን ስጠኝ
እንደተገዛሁልህም አንተ ታውቃለህ አለው። ዘፍ፡ ፳፱ ፳።
ላባም በፊትህ በለሟልነትንስ ካገኘሁ በንተ ምክንያት
እግዚአብሔር እንዳከበረኝ አውቃለሁና። ዘፍ፡ ፴፱ ፫ ፭።
የምሰጥህን ዋጋ ለይልኝ።
ያዕቆብም የተገዛሁልህን አታውቅምን? ከኔ ዘንድ ያሉ
ከብቶችህ ምን ያህል ነበሩ? ዘፍ፡ ፴፩ ፮። ማቴ፡ ፳፱ ፶፩።
ጥቂቶች አልነበሩምን ፡ አሁን ግን ፈጽመው በዝተ
ዋል ፡ በኔ መምጣት እግዚአብሔር አበዛቸው አሁንም እኔ
ለራሴ ቤት ሠርቼ ኀጀ የምወጣ መቼ ነው? አለው ።
ላባም የምሰጥህ ምንድር ነው? አለው ፡ ያዕቆብም
ምንም የምትሰጠኝ ነገር የለም ፡ አሁን ወደ ፊት የምነግ
ርህን ነገር ካደረግህልኝ ዳግመኛ በጎችህን ፈጽሜ እጠብ
ቃለሁ ። ዘፍ፡ ፴፩ ፰ ።
አሁን በጎችህ በፊት ይለፉና ከበጎችህ ሁሉ ጠጕ
ራቸው ነጫጭ የሆኑትንና መልካቸው ዝንጕርጕር የሆ
ነውንም ስለ ዋጋዬ ለይልኝ አለው ።
ዓይነቱ ዝንጕርጕር ያልሆነውና መልኩ ነጭ ያልሆ
ነው ሁሉ ግን ላንተ ይሁን አለው ።
ላባም እንዳልከው ይሁን አለው ።
በዚያችም ቀን ነጩንም ቀዩንም ዝንጕርጕሩንም
መልኩ ዳንግሌ የሆነውንም የፍየሉን አውራ ለይቶ

ቀይሕ ኅብሩ ወወሀበሙ ለደቂቁ ።
፴፮ ወርኀቀ ምሕዋረ ሠሉስ መዋዕል ማእከሎሙ ወማእከለ ያዕቆብ፤ ወያዕቆብሰ ይርዒ አባግዐ ላባ ዘተርፉ ።

፴፯ ወነሥአ ሎቱ ያዕቆብ በትረ ዘልብን ሐመልሚለ ወዘከርከዕ ዐቢየ ወለሐጸ ያዕቆብ ወአሰሰለ ቅርፍቶ ወአስተርአየ ፀዐዳሆን ለእማንቱ፤አብትር እለ ለሐጸ ።
፴፰ ወወደዮን ለእማንቱ አብትር ውስተ ገብላት ዘምስታየ ማይ ከመ ሶበ መጽአ እማንቱ አባግዕ ይስተያ ማየ ይኩና ቅድሜሆን እማንቱ አብትር ።
፴፱ ወሶበ መጽአ እማንቱ፤አባግዕ ወሰትያ ፀንሳ በአርአያሆን ለእማንቱ አብትር፤ ወወለዳ አባግዐ ፀዐዳ ወዘኅብረ ሐመድ ወኲሳኵስ ።
፵ ወቤጸ ያዕቆብ ተባዕተ አባግዒሁ ወፈለጠ አባግዐ ወአቀሞን ቅድመ አብሓኵ ፀዐዳ ወዘኅብረ ሐመድ ወፈለጠ መራዕየ እንተ ባሕቲቶን ወኢደመሮን ምስለ አባግዐ ላባ።

፵፩ ወእምዝ እንከ አመ መዋዕል በዘበቱ ይፀንሳ እማንቱ አባግዕ ይሠይሞን ያዕቆብ ለእማንቱ አብትር ቅድመ አባግዕ ውስተ ገብላት ከመ ይዕንሳ በአርአያሆን ለእማንቱ አብትር ።
፵፪ ወእምከመ ወለዳ እማንቱ አባግዕ ኢይሠይሞን እንከ ወከነ ኵሉ ዘበቱ ትእምርት ለያዕቆብ፤ ወዘአልቦ ትእምርት ለላባ ።
፵፫ ወብዕለ ያዕቆብ ጥቀ ፈድፋደ ወአጥረየ አግብርተ ወአእማተ ወብዙኀ እንስሳ አልሕምተ ወአባግዐ፤ አግማለ ወአእዱገ ።

ምዕራፍ ፴፩ ።

፩ ወሰምዐ ያዕቆብ ነገሮሙ ለደቂቀ ላባ ዘይቤሉ ነሥአ ያዕቆብ ኵሎ ንዋየ አቡነ ወእምንዋየ አቡነ አጥረዮ ለዝንቱ ኵሉ ክብር ።
፪ ወርእዮ ያዕቆብ ለላባ ከመ ኢኮነ ከመ ትካት ገጹ ምስሌሁ ።
፫ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለያዕቆብ ሑር ወግባእ ብሔረ አቡከ ወአዝማዲከ ወአነ እሄሉ ምስሌከ ።
፬ ወጸውዖን ያዕቆብ ለልያ ወለራኄል ውስተ ሐቅል ኀበ ምርዓይ ።
፭ ወይቤሎን ናሁ አነ እሬኢ ገጾ ለአቡክን ከመ ኢኮነ ምስሌየ ከመ ትካት ወአምላኩ ለአቡየ ሀሎ ምስሌየ ።

፮ ተአምራ ከመ በኵሉ ኀይልየ ተቀነይኩ ለአቡክን ።

፯ ወአቡክንሰ አኀዘነኒ ወወለጠ ዐስብየ ዓሠርተ ጊዜ፤ ወኢያብሖ እግዚአብሔር ያኅሥም ላዕሌየ ።

፰ ወለእመ ይቤለኒ ዘኀብር ይኩን ዐስብከ ይወልዳ ኵሎን አባግዕ ዘኀብር፤ ወለእመ ይቤለኒ ፀዐዳ ይኩን ዐስብከ

ለልጆቹ ሰጣቸው ።
በነሱና በያዕቆብ መካከል ሦስት ቀን የሚያስኬድ ጉዳና ርቀው ሄዱ፤ ያዕቆብ ግን የቀሩትን የላባ በጎች ይጠብቅ ነበር ። ዘፍ፡ ፴፩ ፴ ።
ያዕቆብ የልምጭ በትርና ታላቅ የሎሚ በትር ወስዶ ቅርፍቱን ልጦ ጣለው፤ ያዕቆብ የላጣቸው በትሮች ነጫጭ ሁነው ታዩ ።
እነዚያንም በትሮች በጎች ከሚጠጡበት ገንዳ ላይ ጣላቸው፤ በጎቹ ውኃ ሊጠጡ በመጡ ጊዜ እነኛ በትሮች በፊታቸው ሆነው ይታዩ ዘንድ ።
መጥተውም በጠጡ ጊዜ እነዚያን በትሮች አስመስለው ፀንሰው ነጩንና ሐመደ ከበውን ዝንጉርጉሩን ወለዱ ።

ያዕቆብም አውራ አውራዎቹን በጎች ለየ አውራ አውራውን ከለየ በኋላ እንስት እንስቲቱን በጎች ለይቶ ዝንጉርጉር ሐመደ ከበና ነጭ በሚሆኑ አውራዎች ፊት አቆማቸው፤ የራሱንም በጎች ለብቻቸው ለየ እንጂ ከላባ በጎች ጋር አልጨመራቸውም ።
ከዚህ በኋላ በጎቹ በሚፀንሱበት ወራት ያዕቆብ እሊያን በትሮች በበጎቹ ፊት ለፊት በገንዳው ውስጥ ያኖራቸው ነበር፤ እሊያን በትሮች አስመስለው ይፀንሱ ዘንድ።

በጎቹ ከወለዱ በኋላ ግን እሊያን በትሮች በገንዳው ላይ አያኖራቸውም ነበር፤ ምልክት ያለው ሁሉ ለያዕቆብ፤ ምልክት የሌለው ለላባ ሆነ ።
ያዕቆብ እጅግ ፈጽሞ በለጸጋ ሆነ ሴቶችም ወንዶችንም አገልጋይዎች ገዛ፤ ብዙ ከብት ላሞችንም በጎችንም ግመሎችንና አህዮችን ገዛ ። ኢዮብ ፩ ፫ ። መክ፡ ፪ ፯ ።

ምዕራፍ ፴፩ ።

ያዕቆብ የላባ ልጆች፤ የአባታችን የላባን ገንዘብ ሁሉ ወሰደው ከአባታችን ገንዘብ የተነሣ ይህን ሁሉ ክብር አገኘ ያሉትን ሰማ ። ኢዮብ ፰ ፬ ። ምሳ፡ ፲፭ ፴ ።
ያዕቆብ የላባ ፊቱ እንደ ቀድሞው ከሱ ጋር እንዳይደለ አየው ።
እግዚአብሔርም ያዕቆብን እኔ ከንተ ጋር አለሁና ወደ አባትህና ወደ ዘመዶችህ አገር ተመልሰህ ግባ አለው ።
ያዕቆብ ልያንና ራኄልን በጎቹን ወደ ሚያሠማራበት በረኻ ጠራቸው ። ዘፍ፡ ፳፰ ፲፭ ።
እነሆ እኔ የአባታችሁ ፊት እንደ ቀድሞው ከኔ ጋር እንዳልሆነ አያለሁ የአባቴ ፈጣሪ ግን ከኔ ጋር አለ አላቸው ። ኢሳ፡ ፵፩ ። ዕብ፡ ፲፫ ፭ ።
እኔ በሙሉ ጕልበቴ ለአባታችሁ እንዳገለገልኩ ታውቃላችሁ ። ዘፍ፡ ፴ ፳፱ ።
አባታችሁ ግን አሥር ጊዜ ያገልግሎቱን ዋጋ እየለዋወጠ አሳዘነኝ፤ እግዚአብሔር ግን በኔ ላይ ክፉ እንዲያደርግ አላሠለጠነውም ። ኢዮብ ፲፱ ፫ ። ምሳ፡ ፴ ፭ ።
ዝንጕርጕር ሲወለድ ዋጋህ ይሁን ቢለኝ በጎቹ ሁሉ ዝንጕርጕር ይወልዳሉ፤ ዋጋህ ነጭ ይሁን ቢለኝ ሁሉም

ይወልዳ ኵሉን ፀዐዳ ።

ነጭ ይወልዳሉ ። ዘፍ፡ ፴ ፴፱ ።

፱ ወነሥአ እግዚአብሔር ኵሎ አባግዒሁ ለአቡክን ወወሀበኒዮን ሊተ ።

እግዚአብሔር ያባታችሁን በጎች ሁሉ ለይቶ ለኔ ሰጠኝ ።

፲ ወእምዝ አመ ይፀንሳ እሬኢ በአዕይንትየ በሕልም መናሁ አብሓኦ ዘአባግዕ ወዘአጣሊ የዐርጉ ዲበ አባግዕ ወዲበ አጣሊ ፀዐዳ ወዘኅብረ ሐመድ ወዘኰሳኵስ ።

ከዚህም በኋላ በሚፀንሱበት ጊዜ እነሆ የበጎቹ አውራዎች ከበጎቹ የፍየሎቹም አውራዎች ከፍየሎቹ በነጩም በሐመደ ከበውም በዝንጕርጕሩም ላይ ሲንጠላጠሉ በሕልም በዓይኔ አያለሁ ።

፲፩ ወይቤለኒ እግዚአብሔር በሕልም "ያዕቆብ ያዕቆብ" ወእቤ ነየ አነ ምንትኑ ።

እግዚአብሔር በሕልም "ያዕቆብ ያዕቆብ„ ብሎ ጠራኝ ፤ እኔም እነሆ እኔ አለሁ ፤ ምንድር ነው ፤ አልኩ ።

፲፪ ወይቤለኒ ነጽር በአዕይንቲከ ወርኢ አብሓኦ ዘአባግዕ ወዘአጣሊ የዐርጉ ዲበ አባግዕ ወዲበ አጣሊ ፀዐዳ ወዘኅብረ ሐመድ ወዘኰሳኵስ እስመ ርኢኩ ኵሎ ዘይገብር ላዕሌከ ላባ ።

የበጎቹ አውራዎች ከበጎቹ የፍየሎቹ አውራዎች ከፍየሎቹ በነጩም በዝንጕርጕሩም በሐመደ ከበውም ላይ ሲንጠላጠሉ በዓይንህ ተመልከት ፤ ላባ በአንተ ላይ የሚያደርገውን ሁሉ አይቻለሁና አለኝ። ዘፀ፡ ፫ ፯። መዝ፡ ፲፪ ፭።

፲፫ አነ ውእቱ እግዚአብሔር አምላክከ ዘአስተርአይኩከ በብሔር በኀበ ቀባእከ ሊተ ሐውልተ ወበሀየ በፃዕከ ሊተ ብፅዓተ ፤ ወይእዜኒ ተንሥእ ወሑር ውስተ ብሔር ኀበ ተወለድከ ወአነ እሄሉ ምስሌከ ።

ዘይት ያፈሰስክበትን ድንጊያ በቆምክበት ለኔም ስለትን በተሳልክበት በታ የታየሁህ ፈጣሪህ እግዚአብሔር እኔ ነኝ ፤ አሁንም ከዚህ ተነሥተህ ወደ ተወለድክበት አገር ሂድ ፤ እኔም ካንተ ጋር እኖራለሁ አለኝ አላቸው ።

፲፬ ወአውሥኣሁ ወይቤላሁ ቦኑ እንከ ዘብነ ርስት ውስተ ቤተ አቡነ ።

እነሱም እንዲህ ብለው መለሱለት ፤ እንግዲህ ወዲህ በአባታችን ቤት የምናገኘው ርስት በውኑ አለን ?

፲፭ አኮኑ ከመ ነኪር ንሕነ በኀቤሁ ወሤጠነ ወበልዐ ሤጠነ ።

በርሱ ዘንድ እንደ ባዕድ አይደለንምን ፤ እኛንስ ሸጦ ዋጋችንን የበላ አይደለምን ! ።

፲፮ ወዝ ኵሉ ክብር ዘነሥአ እግዚአብሔር እምአቡነ ለነ ውእቱ ወለውሉድነ ፤ ወይእዜኒ ግበር ኵሎ ዘይቤለከ እግዚአብሔር ።

ይህ ሁሉ ሃብት እግዚአብሔር ከአባታችን ነሥቶ የሰጠህ ለኛም ለልጆቻችንም ነው ፤ አሁንም እግዚአብሔር ያለህን አድርግ አሉት ።

፲፯ ወተንሥአ ያዕቆብ ወነሥአ አንስቲያሁ ወደቂቆ ወጸዐኖሙ ዲበ አግማል ።

ያዕቆብም ሚስቶቹን ይዞ ልጆቹን በግመሎች ጭኖ ተነሣ ።

፲፰ ወነሥአ ኵሎ መራዕይሁ ወቄሳቍሳቲሁኒ ዘአጥረየ በማእከለ አፍላግ ወኵሎ ዘዚአሁ ወሖረ ኀበ አቡሁ ይስሐቅ ውስተ ምድረ ከነአን ።

በሁለቱ ወንዞች መካከል ባለው በሶርያ ያፈራቸው መንጋዎቹን ታላላቁንና ታናናሹን ገንዘቡን ሁሉ ይዞ ወደ አባቱ ወደ ይስሐቅ ወደ ከነዓን አገር ሄደ ። ዘፍ፡ ፴፭ ፪ ።

፲፱ ወላባሰ ሖረ ኀበ ይቀርፅ አባግዒሁ ወሰረቀት ራኄል አማልክተ አቡሃ ።

ላባ ግን በጎቹ ወደሚሸልትበት በታ ሂዶ ነበር ፤ ራኄልም ያባቷን ጣኦቶች ሰረቀች ።

፳ ወያዕቆብሰ ኀብአ ለላባ ሶርያዊ ወኢያይድዖ ከመ የሐውር ።

ያዕቆብም ለሶርያው ሰው ለላባ ሠወረው እንጂ እንደ ሚሄድ አልነገረውም ነበር ።

፳፩ ወሖረ ውእቱ ወኵሉ ዘዚአሁ ወዐደወ ፈለገ ወኀደረ በደብረ ገለዓድ ።

እሱም የሉንም ወገኖች ሁሉ ይዞ ሄደ ፤ ወንዙንም ተሻግሮ በገለአድ ተራራ አደረ ።

፳፪ ወዜነውዎ ለላባ ሶርያዊ ከመ ሖረ ያዕቆብ ።

ለሶርያዊው ላባም ያዕቆብ እንደ ሄደ ነገሩት ።

፳፫ ወነሥአሙ ላባ ለኵሎሙ አኀዊሁ ወዴገኖሙ ምሕዋረ ሠሉስ መዋዕል ወረከቦሙ በደብረ ገለዓድ ።

ላባም ወንድሞቹን ሁሉ ይዞ የሦስት ቀን ጕዳና ተከትሎ በገለአድ ተራራ አገኛቸው ።

፳፬ ወመጽአ እግዚአብሔር ኀበ ላባ ሶርያዊ በሕልም ሌሊተ ወይቤሎ ዑቅ ኢትንብብ ኅሡመ ላዕለ ያዕቆብ ገብርየ ።

እግዚአብሔርም ሌሊት በሕልም ወደ ሶርያዊው ሰው ወደ ላባ መጥቶ ፤ በወዳጄ በያዕቆብ ላይ ክፉ ነገር እንዳትናገር ተጠንቀቅ አለው ። ዘፍ፡ ፳ ፫ ። ማቴ፡ ፩ ፳ ።

፳፭ ወረከበ ላባ ለያዕቆብ ፤ ወያዕቆብሰ ይተክል ሐይመቶ ውስተ ደብር ወአቀሞሙ ላባ ለአኃዊሁ ውስተ ደብረ ገለአድ ።

ላባም ያዕቆብን አገኘው ፤ ያዕቆብ ግን ድንኳኑን በተራራው ላይ ተክሎ ሰፍሮ ነበር ፤ ላባም ወንድሞቹን በገለአድ ተራራ ላይ አቆማቸው ሄደ ።

፳፮ ወይቤሎ ላባ ለያዕቆብ ምንተ ገበርኩ ጽሚተ ዘትትኀጥአኒ ወትሰርቀኒ አዋልድየ ከመ ዘበኲናት ፄወወ ።

ላባ ያዕቆብን እንዲህ አለው ፤ ተሠውረኸኝ ኰብልለህ የመጣህ ምን አደረግሁህ በጦር እንደ ማረከ ሰው ፤ ልጆቼንስ ለምን ሰረቅኸኝ ? አለው ። ፩ ሳሙ፡ ፴ ፪ ።

፳፯ ወሶበ ነገርከኒ እምፈነውኩከ በትፍሥሕት ወበኃሤት ወበማኅሌት ወበከበሮ ወበመሰንቆ ።

ነግረኸኝስ ቢሆን በፍጹም ደስታ በዘፈን በጨዋታ ከበሮውን መሰንቆውን እያስመታሁ በሸኘሁህ ነበር ።

፳፰ ወሚመ ኢይደልወኒኑ ከመ እስዐም ደቂቅየ ወአዋልድየ፡ ወይእዜሰ ከመ ዐብድ ገበርከ ።

ወይስ ወንዶች ልጆቼን ሴቶች ልጆቼን ስሚ ሸኝቼ መሰናበት አይገባኝም ነበርን፡ አሁንም እንደ አላዋቂ ሰው ሥራ ሠርተሃል ። ፩ ነገ፡ ፲፱ ፳ ።

፳፱ ወይእዜኒ እምክህልኩ ገቢረ እከይ ላዕሌከ ወባሕቱ አምላከ አቡከ ይቤለኒ ትማልም ዑቅ ርእሰከ ኢትግበር ኅሡመ ላዕለ ያዕቆብ ።

አሁንም በንተ ላይ ክፉ ነገር ላደርግ በተቻለኝ ነበር፡ ነገር ግን ያባትህ ፈጣሪ ትናንት በያዕቆብ ላይ ክፉ እንዳ ትሠራ ስራስህ ተጠንቀቅ ብሎ ቢነግረኝ ነው እንጂ ።

፴ ወይእዜኒ ሑር እመ ፈተውከ ከመ ትሑር ቤተ አቡከ ወለምንት ትሰርቀኒ አማልክትየ ።

አሁን ግን ወደ አባትህ ቤት መሄድን ከወደድክ ሂድ አለው፡ በዚያውስ ላይ አማልክቶቼን ለምን ሰረቅኸኝ፡ አለው ።

፴፩ ወአውሥአ ያዕቆብ ወይቤሎ ለላባ እስመ መሰለኒ ዘተኃይደኒ አዋልዲከ ወኵሎ ንዋይየ፡ ወይእዜኒ ርኢ ለእመ ብ ንዋይከ ኀቤየ ወንሣእ፡ ወበኀበ ዘረከብከ አማልክቲከ ኢይሕየው ።

ያዕቆብም ለላባ እንዲህ ሲል መለሰለት ፤ ልጆችህን ገንዘቤንም ሁሉ የምትቀማኝ ስለ መሰለኝ ነው፡ አሁንም ገንዘብህ ከኔ ዘንድ እንዳለ አይተህ ውሰድ አለው፡ ጣኦቶ ችህን ያገኘህበትም ሰው አይዳን ። መሰ፡ ፲፰ ፳፬ ።

፴፪ ወኢያእመረ ያዕቆብ ከመ ሰረቀት ራሔል ።

እነሆ ያንተ የሆነው ገንዘብ ከኔ ዘንድ ቢገኝ በነዚህ ወንድሞቻችን ፊት አዳኘብሃለሁ ያዕቆብ ግን ራሔል እንደ ሰረቀች አላወቀም ነበር ። ዘፍ፡ ፵፬ ፱ ።

፴፫ ወቦአ ላባ ቤተ ያዕቆብ ወኢረከበ፡ ወወፅአ ወቦአ ቤተ ልያ ወፈተነ ወኢረከበ፡ ወቦአ ቤተ ክልኤሆን ዕቁባቲሁ ወኢረከበ፡ ወቦአ ቤተ ራሔል ።

ላባም ከያዕቆብ ቤት ገብቶ አላገኘም፡ ከዚያም ወጥቶ ወደ ልያ ቤት ገብቶ ቢበረብር ምንም አላገኘም፡ ከሁለቱ ዕቁባቶቹም ቤት ገብቶ በረበረ ነገር ግን ምንም አላገኘም፡ ራሔል ካለችበትም ቤት ገባ ።

፴፬ ወራሔልሰ ነሥአቶሙ ለአማልክተ አቡሃ ወወደየቶሙ ውስተ ሕንበለ ገመል ወነበረት ላዕሌሆሙ ።

ራሔል ግን ያባቷን ጣኦቶች ሠርቃ ከግመል ኮርቻ ውስጥ አግብታ በላዩ ላይ ተቀምጣ ነበር ። ቁ፡ ፲፱ ።

፴፭ ወትቤሎ ለአቡሃ ኢይምሰልከ ዘአስተሐቀርኩከ እግዚእየ እስመ ኢይክል ተንሥአ ቅድሜከ እስመ ትክት አነ ወፈተነ ላባ ኵሎ ቤታ ለራሔል ወኢረከበ አማልክቲሁ ።

አባቱ ከግዳጄ ስላልነጻሁ በፊትህ መነሣት አልቻልምና ነው እንጂ ያቃለልኩህ አይምሰልህ አለችው፡ ላባም የራሔልን ቤት ሁሉ በረበረ፡ ነገር ግን ጣኦቶቹን አላገኘም ።

፴፮ ወተምዐ ያዕቆብ ወተላከዮ ለላባ ወይቤሎ ምንትኑ አበሳየ ወምንትኑ ጌጋይየ ዘዴገንከኒ ወፈተንከኒ ኵሎ ንዋይየ ።

ያዕቆብም ተቈጥቶ ላባን እንዲህ ሲል ተከራከረው፡ ገንዘቤን ሁሉ የበረበርክብኝና የተከተልከኝ በደሌ ዕዳዬ ምንድር ነው፤ ። ፩ ሳሙ፡ ፲፱ ፫ ። ፩ ቆሮ፡ ፮ ፰ ።

፴፯ ወምንተ ረከብከ እምነ ኵሉ ቍስቍሰ ቤትከ ናስተአኅዝኡ ቅድመ እሉ አኀዊነ ወይግዝልፉ ማእከሌነ ።

ከቤትህስ ቁሳቍስ ዕቃ ምን አገኘህ፤ በነዚህ ወንድሞቻችን ፊት እንዋቀስና በመካከላችን ይፍረዱን ።

፴፰ ዕሥራ ወክልኤ ዓመት ሊተ እንዘ አዐቅብ አባግዒከ ወአጣሊከ ወኢመሐስአ በግዕ ኢበላዕኩ እምአባግዒከ ።

ሃያ አንድ ዓመት በጎችህንና ፍየሎችህን ስጠብቅ ኖርኩ ከበጎችህም ጠቦት እንኳ አልበላሁም ። ዘፀ፡ ፳፪ ፲፪።

፴፱ ወብላዐ አርዌኒ ኢያምጻእኩ ለከ፡ ወእፈድየከ እምኀቤየ እመኒ ብ ዘተሰርቀ፡ እመኒ መዓልተ ወእመኒ ሌሊተ በጠሉ አበይት፡ ወነፍጸ ንዋም እምአዕይንትየ ።

አውሬ የነከሰውንም ትራፊ አላመጣሁልህም፡ የተሰረቀም ቢኖር ከኔ እከፍልህ ነበር፡ በቀንም በሌሊትም በጤዛ ተንከራ እኖር ነበር፡ እንቅልፍ ከዓይኖቼ ጠፍቶ ይኖር ነበር ።

፵ ዕሥራ ወክልኤ ዓመት ሊተ ዮም ውስተ ቤትከ ዘተቀነይኩ ለከ ።

በቤትህ የተገዛሁልህ ዛሬ ሃያ አንድ ዓመት ነው ። ዘፍ፡ ፴፩ ፵፩ ።

፵፩ ዓሠርተ ወአርባዕተ ዓመተ ተቀነይኩ ለከ በእንተ ክልኤሆን አዋልዲከ፡ ወሰብዓተ ዓመተ በእንተ አባግዒከ ወአኅለፍከ ብየ ዐስብየ ዓሠርተ ጊዜ ።

ስለ ሁለቱ ልጆችህ ዓሥራ አራት ዓመት ተገዛሁልህ፡ ስለ በጎችህም ፯ት ዓመት ተገዛሁልህ ዋጋዬንም ዓሥር ጊዜ ለዋወጥክብኝ ። ዘፍ፡ ፳፱ ፳፮ ። መዝ፡ ፲፻፬ ፩ ።

፵፪ ወሰበ አኮ አምላከ አብርሃም አቡየ ዘሀሎ ምስሌየ ወሰበ አኮ በፍርሀተ ይስሐቅ ዕራቅየ እምፈነውከኒ ወርእየ እግዚአብሔር የማህምን ለእደውየ ወገሠጸከ ትማልም ።

ያባቴ የአብርሃም ፈጣሪ ከኔ ጋር ባይኖር፡ በአባቴ ይስሐቅ አምልኮት ጸንቼ ባልኖር ባዶዬን በሰደድከኝ ነበር፡ እግዚአብሔር ግን የእጆቼን ድካም አይቶ ትናንት በሕልም ገሠፀህ ።

፵፫ ወአውሥአ ላባ ለያዕቆብ ወይቤሎ ደቂቅከኒ ደቂቅየ ወአዋልዲከኒ አዋልድየ፡ ወእንስሳከኒ እንስሳየ ወዝ ኵሉ ዘትሬኢ ዚአየ ውእቱ ለእላ አዋልድየ ምንተ እንከ እሬስዮን ሎቶን ዮም ወለውሉዶንሂ ዘወለዳ ።

ላባም ለያዕቆብ እንዲህ ሲል መለሰለት ፤ ወንዶቹም ሴቶቹም ልጆችህ ልጆቼ፡ ከብቶችህም ከብቶቼ ናቸው፡ ይህ የምታየው ሁሉ የኔ ገንዘብ ነው፡ እንግዲህ እሊህ ልጆቼን አሁን ምን አደርጋቸዋለሁ ፤ የወለዱዋቸው ልጆ

፵፬ ወይእዜኒ ነዓ ንትማሐል አነ ወአንተ ወይኩን ሰላም
ማእከሌየ ወማእከሌከ ።
፵፭ ወነሥአ ያዕቆብ እብነ ወአቀመ ሐውልተ ።
፵፮ ወይቤሎሙ ያዕቆብ ለአኀዊሁ አልዱ አእባነ ፡ ወአ
ለዱ ወገብሩ ወግረ ወበልዑ ወሰትዩ ዲበ ይእቲ እብነ ወ
ግር ፡ ወይቤሎ ላባ ዛቲ ወግር ስምዕ ማእከሌየ ወማእከሌከ።

፵፯ ወሰመያ ላባ "ወግረ ስምዕ„ ወያዕቆብኒ ሰመያ ከማሁ።

፵፰ ወይቤሎ ላባ ለያዕቆብ ነያ ዛቲ ወግር እንተ አቀውም
ስምዕ ማእከሌየ ወማእከሌከ ፡ ወበእንተ ዝንቱ ተሰምየ
ስማ "ወግረ ስምዕ„ ።
፵፱ ወይቤሎ ላባ ራእየ ዘአስተርአየኒ እግዚአብሔር ይር
አይ ማእከሌየ ወማእከሌከ ዮም እስመ ንትራኃቅ አሐዱ
እምክልኤ ።
፶ ከመ ኢትሣቅዮን ለአዋልድየ ወከመ ኢትንሣእ ብእ
ሲተ ላዕሌሆን ።
፶፩ ወርኢ ናሁ አልቦ ዘሀሎ ምስሌነ ።
፶፪ አመኒ ዐዶኩ ኀቤከ ዛቲ ወግር ወዛቲ ሐውልት ትት
ልወኒ በእኪት ።
፶፫ ወአንተኒ ለእመ ዐዶከ ኀቤየ አምላከ አብርሃም ወአ
ምላከ ናኮር ይፍታሕ ማእከሌየ ወማእከሌከ ፡ ወመሐለ
ሎቱ ያዕቆብ በፍርሀተ ይስሐቅ አቡሁ ።

፶፬ ወሦዐ ያዕቆብ መሥዋዕተ በውስተ ደብር ወጸውዖሙ
ለአኀዊሁ ወበልዑ ወሰትዩ በቤቱ ፡ ወቤቱ ውስተ ውእቱ
ደብር ።
፶፭ ወተንሥአ ላባ በጽባሕ ወሰዐመ አዋልዲሁ ወደቂቆን
ወባረኮሙ ፡ ወተመይጠ ላባ ብሔሮ ወሖረ ።

ምዕራፍ ፴፪ ።

፩ ወያዕቆብኒ ገብአ ውስተ ፍኖቱ ፡ ወነጸረ በአዕይንቲሁ
ያዕቆብ ወርእየ ተዐይነ እግዚአብሔር ኀዱራነ ወተራከ
ብዎ መላእክተ እግዚአብሔር ።
፪ ወይቤ ያዕቆብ ሶበ ርእየ ተዐይነ እግዚአብሔር ይእ
ቲ ዛቲ ፡ ወሰመየ ስሞ ለውእቱ ብሔር ተዐይን ።

፫ ወፈነወ ያዕቆብ ሐዋርያተ ኀበ ዔሳው እኁሁ ብሔረ
ሴይር ውስተ ምድረ ኤዶም ።
፬ ወአዘዞሙ ወይቤሎሙ ከመዝ በልዎ ለዔሳው እግዚ
እየ ፡ ከመዝ ይቤ ገብርከ ያዕቆብ ኀበ ላባ ነበርኩ ወጐን
ደይኩ እስከ ዮም ።
፭ ወአጥረይኩ አግብርተ ወአእማተ ወአልሕምተ ወአባ
ግዐ ፡ አግማለ ወአእዱገ ወፈነውኩ ይዜንውዎ ለእግዚእየ
ዔሳው ከመ እርከብ ሞገሰ በቅድሜከ አነ ገብርከ ።
፮ ወገብኡ ኀቤሁ ለያዕቆብ እሙንቱ ሐዋርያት እለ ፈነ
ወ ወይቤልዎ ሖርነ ኀበ ዔሳው እኁከ ወናሁ መጽአ ይት
ቀበልከ ወአርባዕቱ ምእት እደው ምስሌሁ ።

ቻቸውንስ ምን አደርጋቸዋለሁ ፤
አሁንም እኔና አንተ እንማማል ፡ በኔና በንተ መካ
ከል ሰላም ይሁን አለው ። ዘፍ፡ ፳፭ ፳ ። ኢያሱ ፳፬ ፳፯።
ያዕቆብም ድንጊያን አንሥቶ ሐውልት አቆመ ።
ያዕቆብ ወንድሞቹን ድንጊያ ሰብስቡ ብሎአቸው ሰብ
ስበው ክረብታን ያህል ከመሩ ፡ ሰብስበው በክምሩትም
ድንጊያ ላይ ተቀምጠው በሉ ጠጡ ፡ ላባም ይህች ክረብታ
በኔና በአንተ መካከል ምስክር ናት አለው ።
ክረብታይቱንም "የምስክር ተራራ„ ብሎ ጠራት ያዕቆ
ብም እንዲሁ የምስክር ተራራ ብሎ ጠራት። ኢያ፡ ፳፬ ፳፯፥
ላባም ያዕቆብን ይህች ያቆምኳት ሐውልት በኔና በን
ተ መካከል የምስክር ሐውልት ትሁን አለው ፡ ስለዚህም
ስሟ "የምስክር ክረብታ„ ተባለች ። ኢያሱ፡ ፳፬ ፳፯ ።
ላባ ያዕቆብን በራእይ የተነጋገረኝ እግዚአብሔር ዛሬ
በኔና በንተ መካከል ምስክር ነው ፡ እርስ በርሳችን አንዱ
ከንዱ ተራርቀን እንኖራለንና ። መሳ፡ ፲፩ ፳፱ ።
በላያቸው ላይ ሴት አግብተህ ልጆቼን እንዳታሳዝና
ቸው በኔና በንተ መካከል እግዚአብሔር ይፍረድ አለው።
አሁን ከኛ ጋር ሌላ ሰው እንደሌለ አስተውል ።
እኔ መሐላዬን አፍርሼ በክፋት ወዳንተ ብሻገር ይህች
ተራራና ሐውልት በክፋት ትከተለኝ ።
አንተም መሐላህን አፍርሰህ በክፋት ወደኔ ብትመጣ
የአብርሃምና የናኮር ፈጣሪ በኔና በንተ መካከል ይፍረድ
አለው ፡ ያዕቆብም አባቱ ይስሐቅ በሚያመልከው በእግዚ
አብሔር ስም ማለ ። ዘፍ፡ ፲፯ ፫ ።
ያዕቆብ በተራራው ላይ መሥዋዕትን ሠውቶ ወንድ
ሞቹን በቤቱ ጠርቶ በልተው ጠጥተው በዚያው ተራራ
ላይ አደሩ ።
ላባም ማለዳ ተነሥቶ ልጆቹን የልጅ ልጆቹን ስሞና
መርቆ ተመልሶ ወደ አገሩ ሄደ ።

ምዕራፍ ፴፪ ።

ያዕቆብም ወደ መንገዱ ተመለሰ ፡ ያዕቆብ በዓይኖቹ
ተመልክቶ የእግዚአብሔርን ሠራዊት ከትመው አየ ፡ የእ
ግዚአብሔር መላእክትም ተገናኙት ። መዝ፡ ፺፩ ፲፩ ።
ያዕቆብም ይህን በየ ጊዜ ይህች የእግዚአብሔር ከተማ
ናት አለ ፡ የዚያን ቦታ ስም የእግዚአብሔር ከተማ ብሎ
ጠራ ። መዝ፡ ፺፫ ፳፩ ።
ያዕቆብ በኤዶም ውስጥ ወዳለች ወደ ሴይር ከወን
ድሙ ዘንድ መልእክተኛ ላከ ። ዘዳ፡ ፪ ፭ ። ኢያሱ፡ ፳፬ ፬።
ጌታዬ ዔሳውን አገልጋይህ ያዕቆብ ከላባ ዘንድ እኖር
ነበር ፡ እስከ ዛሬ ድረስም ዘገየሁ በሉት ብሎ አዘዛቸው ።
ምሳ፡ ፲፭ ፩ ።
ወንዶችም ሴቶችም አገልጋዮች ፡ ላሞችም አህዮችም
ግመሎችም አገኘሁ ፡ እኔ አገልጋይህ በፊትህ ባለሟልነ
ትን አገኝ ዘንድ ለጌታየ ለዔሳው ሊነግሩት ዘንድ ላክሁ ።
የላካቸውም መልእክተኞች ተልእኳቸውን አድር
ሰው ወደ ያዕቆብ ተመለሱ ፡ ወደ ወንድምህ ወደ ዔሳው
ሄደን የላክኸንን ነገርነው ፡ እሱም አሁን አራት መቶ ሰው

አስከትሎ ሊቀበልህ መጥቷል። ዘፍ፡ ፴፫ ፩።

፯ ወፈርሀ ጥቀ ያዕቆብ ወኀጥአ ዘይገብር ወነፈቆሙ ለሕዝብ እለ ምስሌሁ ወለአባግዕኒ ወለአልሕምትኒ ወለአግማልኒ ወገብሮሙ ክልኤተ ትዕይንተ።

ያዕቆብም እጅግ ፈርቶ ተጨነቀ የሚያደርገውን አጣ ከሱ ጋር ያሉትን ከሁለት ከፈላቸው፤ ላሞችንም በጎችንም ግመሎችንም ሁለት ሁለት ወገን አድርጎ ከፈላቸው።

፰ ወይቤ ያዕቆብ ለእመ መጽአ ዔሳው ውስተ አሐቲ ትዕይንት ወቀተላ ትድኅን ካልእት ትዕይንት።

ያዕቆብ ዔሳው መጥቶ አንዲቱ ሰፈር ቢያጠፋ አንዲቱ ሰፈር ትድናለች ብሎ ከሁለት ወገን ከፈላቸው።

፱ ወይቤ ያዕቆብ ውእቱ አምላክ አበውየ አምላክ አብርሃም ወአምላክ ይስሐቅ ዘይቤለኒ ሑር ውስተ ብሔር ኀበ ተወለድከ ወአነ አሤኒ ላዕሌከ ያሤኒ እንከሰ ላዕሌየ።

ወደ ተወለድክበት አገር ሂድ ላንተ በጎ ነገርን አደርግልሃለሁ ያለኝ ያባቶቼ የአብርሃም የይስሐቅ ፈጣሪ እግዚአብሔር አሁ በጎ ነገርን ያደርግልኛል አለ። መዝ፡ ፺ ፲፩።

፲ ወበዙሉ ጽድቅ ወርትዕ ዘገበርከ ለገብርከ ረከብኩ፤ እስመ በበትርየ ዐደውክዎ ለዝንቱ ዮርዳኖስ ወይእዜሰ ከንኩ ክልኤተ ተዐይነ።

ከዚህም በፊት ለኔ ላገልጋይህ በደረግኸው ቸርነትና ቅንነት ሁሉ በለሟልነትን አግኝቻለሁ፤ ይህን ዮርዳኖስን ከበትሬ ጋር ተሻግሬው ነበርና ዛሬ ግን ሁለት ጭፍራ ለመሆን በቃሁ። ፪ ሳሙ፡ ፱ ፳። ዘፍ፡ ፳፱ ፳፯።

፲፩ ወአድኅነኒ እግዚኦ እምእዴሁ ለዔሳው እኁየ፤ እስመ እፈርሆ አነ እምኔሁ ላዕለ ርእስየ ከመ ኢይምጻእ ወኢይቅትለኒ ወኢይቅትል እመ ምስለ ውሉዳ።

አሁንም ከወንድሜ ከዔሳው እጅ አድነኝ መጥቶ እንዳይገድለኝ ከሱ የተነሣ ለራሴ እፈራለሁና፤ እናትን ከልጆቿ ጋር እንዳይገድል አለ። መዝ፡ ፶፱ ፩-፪።

፲፪ እስመ ትቤለኒ አሤኒ ላዕሌከ ወእሬሲ ዘርእከ ከመ ኆፃ ባሕር ዘኢይትኌለቍ እምብዝኁ።

በጎ ነገርን አደርግሃለሁ ብለኸኛልና፤ ከብዛቱም የተነሣ የልጅ ልጅህን እንደማይቈጠር አሸዋ አደርገዋለሁ ብለኸኝ ነበርና። ዘፍ፡ ፳፰ ፲፫ ፲፭።

፲፫ ወቤተ ህየ በይእቲ ሌሊት ወአውፅአ አምኃ ዘይወስድ ለዔሳው እኁሁ።

በዚያችም ሌሊት ከዚያ አደረ፤ ለወንድሙ ለዔሳው የሚወስደውን እጅ መንሻ ሁለት መቶ እናት ፍየል፤ ሃያ የፍየል አውራ አወጣ። ዘፍ፡ ፵፫ ፲፩።

፲፬ ክልኤተ ምእተ አጣሌ፤ ወዕሥራ አብሓኰ አጣሊ፤ ወክልኤተ ምእተ አባግዐ፤ ወስሳ አብሓኰ አባግዕ።

ሁለት መቶ ፍየሎች፤ ሃያ የፍየል አውራዎች ሁለት መቶ እናት በጎች፤ ስድሳ የበጎች አውራዎች አወጣ።

፲፭ ኃምሳ ናቃተ ምስለ እጕሊሆን፤ ወአርብዐ ዕጐልተ፤ ወዐሠርተ አሥዋረ፤ ወዕሥራ እእዱግ ወዐሠርተ ዕዋለ።

አምሳ ግመሎች ከነጥጆቻቸው፤ አርባ ሚዜ፤ ዓሥር ገቾ፤ ሃያ አህዮች፤ ዓሥር የአህያ ግልገሎች አወጣቶ።

፲፮ ወወሀቦሙ ለደቂቁ መራዕየ እንተ ባሕቲቶሙ ወይቤሎሙ ሑሩ ቅድመ ወአስተራኅቁ መራዕየ እመራዕይ።

ለብላቴኖቹ ሰጣቸው መንጋውን ከመንጋ ለይታችሁ እያራራቃችሁ በፊት በፊቴ ሂዱ አላቸው።

፲፯ ወአዘዘ ለቀዳማዊ ወይቤሎ ለእመ ረከበከ ለዔሳው እኁየ ወተስእለከ ወይቤለከ ዘመኑ ዝንቱ ወአይቴ ተሐውር ወዘመኑ ዝ ዘየሐውር ቅድሜከ።

ፊተኛውንም እንዲህ ብሎ አዘዘው፤ ወንድሜ ዔሳው አግኝተኸው ይህ መንጋ የማን ነው፤ ብሎ የጠየቀህ እንደሆነ የት ትሄዳለህ ያለህም እንደሆነ በፊትህስ የሚሄደው ይህ መንጋ የማነው፤ ብሎ ቢጠይቅህ።

፲፰ በሎ ዘገብርከ ያዕቆብ አምኃ ዘፈነወ ለእግዚኡ ዔሳው ወናሁ ውእቱኒ ይተልወነ ድኅሬነ።

አገልጋይህ ያዕቆብ ለጌታው ለዔሳው የላከው እጅ መንሻ ነው፤ እሱም አሁን በኋላችን ይከተለናል በለው አለው።

፲፱ ወአዘዘ ለካልኡኒ ወለሣልሱኒ ወለኵሎሙ እለ የሐውሩ ቅድሜሁ ወይነድኡ መራዕየ ወይቤሎሙ ለእመ ረከብክምዎ ለዔሳው እኁየ ከመዝ በልዎ ናሁ ገብርከ ያዕቆብ ይበጽሕ ድኅሬነ።

ሁለተኛውንና ሦስተኛውንም አካች በፊት በፊቱ መንጋ እየነዱ የሚሄዱትንም ሁሉ ወንድሜ ዔሳውን ያገኛችሁት እንደሆነ፤ እነሆ አገልጋይህ ያዕቆብ በኋላችን ይመጣል በሉት ብሎ አዘዛቸው።

፳ እስመ ይቤ አድኅን እምገጹ በዝንቱ አምኃ ዘይወስዱ ደቅ ቅድሜሁ ወእምዝ እሬኢ ገጾ ቅድመ ከመ ይትቀበሎ ለገጽየ በዳኅን።

በፊቱ በሚወስዱት በዚህ እጅ መንሻ ከወንድሜ ከፊቱ ቍጣ እድናለሁ ብሏልና፤ ከዚህ በኋላ ፊቱን ደስ ብሎት አያለሁ፤ እኔንም በደኅና ይቀበለኛል ብሎ ነው።

፳፩ ወእምዝ ፈነወ አምኃ ወውእቱሰ ቤተ ውስተ ትዕይንት በይእቲ ሌሊት።

ከዚህ በኋላ እጅ መንሻውን ላከ፤ እርሱ ግን በዚያች ሌሊት በሰፈር አደረ።

፳፪ ወተንሥአ ያዕቆብ ወነሥአን ለክልኤሆን አንስቲያሁ ወለክልኤሆን ዕቁባቲሁ ወዐሠርተ ወአሐደ ደቂቆ ወዐደወ ማዕዶተ ያቦቅ።

ያዕቆብ ተነሥቶ ሁለቱ ሚስቶቹን ሁለቱ ዕቁባቶቹንና ዓሥራ አንድ ልጆቹን ይዞ የያቦቅን ወንዝ ተሻገረ፤ ዘዳግ፡ ፫ ፲፯።

ወነሥኦሙ ወዐደወ ውኂዘ ወአዕደወ ኵሉ ንዋያቲሁ።

ይዞአቸውም ወንዙን ተሻገረ ጓዙንም ሁሉ አሻገረ።

| | | |
|---|---|---|
| ወተርፈ ያዕቆብ ባሕቲቱ ወተጋደሎ ብእሲ እስከ ጽባሕ ። | ፳፬ | ያዕቆብ ብቻውን ቀረ እስከንጋት ድረስ አንድ ሰው ሲታገለው አደረ ፤ ፪ ቆሮ. ፲፪ ፯ ። |
| ወሶበ ርእየ ከመ ኢይክሎ አኀዘ ሥርዐ ሐቌሁ እንዘ ይትጋደል ምስሌሁ ። | ፳፭ | ከርሱም ጋር ሲታገል እንዳልቻለው በየ ጊዜ ፤ ከርሥ የሚሆንበት ሹልዳውን ያዘው ። |
| ወይቤሎ ፈንወኒ እስመ ጎህ ጽባሕ ፤ ወይቤሎ ኢይፌንወከ እስመ ኢባረከኒ ። | ፳፮ | ጎህ ቀድዷልና ልቀቀኝ አለው ፤ ካልመረቅከኝ አልለ ቅህም አለው ፤ ሉቃ. ፳፬ ፳፰ ። |
| ወይቤሎ መኑ ስምከ ወይቤሎ ያዕቆብ ስምየ ። | ፳፯ | ስምህ ማን ይባላል ፤ ቢለው ፤ ስሜ ያዕቆብ ነው አለው ። |
| ወይቤሎ ኢይኩን እንከ ስምከ ያዕቆብ ፤ ዳዕሙ ይኩን ስምከ "እስራኤል" እስመ ክህልከ ምስለ እግዚአብሔር ወምስለ እጓለ እመሕያው ። | ፳፰ | እንግዲህ ወዲህ ስምህ ያዕቆብ አይባል ፤ "እስራኤል" ይባል እንጂ አለው ፤ ከእግዚአብሔርና ከሰውም ጋር መታገልን ችለሃልና ፤ ሆሴ. ፲፪ ፬ ። |
| ወይቤሎ ያዕቆብ አይድዐኒ ስመከ ፤ ወይቤሎ ለምንት ለከ ትሴአል ስምየ እስመ መድምም ውእቱ ወባረኮ በህየ ። | ፳፱ | ያዕቆብም ስምህን ንገረኝ አለው ፤ ስሜን ለምን ትጠይቃለህ ፤ ስሜ መድምም (ድንቅ) ነውና ፤ በዚያም ቦታ ባረከው ። |
| ወሰመዮ ያዕቆብ ስመ ለውእቱ ብሔር ፤ "ራእየ እግዚአብሔር" እስመ ይቤ ርኢክዎ ለእግዚአብሔር ገጸ በገጽ ወድኅነት ነፍስየ ወገጽየ ። | ፴ | ያዕቆብ የዚያን ቦታ ስም "የእግዚአብሔር መገለጫ" ብሎ ጠራው እግዚአብሔርን ፊት ለፊት አይቸዋለሁና ፤ ከዚህም የተነሣ ሰውነቴም ፊቴም ድናለችና ፤ ዘፍ. ፲፮ ፲፫ ። |
| ወሠረቀ ፀሐይ ሶበ ኀደጎ ራእየ እግዚአብሔር ወሎቀሰ ያስአንክስ እግሩ ። | ፴፩ | ፀሐይም በወጣ ጊዜ የእግዚአብሔር መገለጥ ተወው እሱንም ሹልዳው ያደነዝዘው ነበር ። |
| ወበእንተዝ ኢይበልዑ ደቂቀ እስራኤል እስከ ዛቲ ዕለት ውእተ ሥርወ ዘአስአንክሶ ዘሀሎ ውስተ ዓወ እግሩ እስመ አኀዘ ሥርዐ ሐቌሁ ለያዕቆብ ውስተ ሥርው ኀሩም ። | ፴፪ | ስለዚህም የእስራኤል ልጆች በእግሩ መካከል ያለ የደነዘዘውን ሹልዳ እስከ ዛሬ ድረስ አይበሉም የያዕቆብ ሹልዳው ደንዝዞበት ነበርና ፤ ይህ ሹልዳ ለእስራኤል ልጆች እርም ነው ። |

| ምዕራፍ ፴፫ ። | | ምዕራፍ ፴፫ ። |
|---|---|---|
| ወአንሥአ ያዕቆብ አዕይንቲሁ ወርእየ ወናሁ ኤሳው እኁሁ መጽአ ወአርባዕቱ ምእት እደው ምስሌሁ ፤ ወነፈቆሙ ያዕቆብ ለደቂቁ ኀበ ልያ ወኀበ ራኄል ወኀበ ክልኤሆን ዕቁባቲሁ ። | ፩ | ያዕቆብም ዓይኖቹን አቅንቶ አየ ፤ እነሆም ወንድሙ ዔሳው አራት መቶ ሰዎችን ይዞ ሲመጣ ተመለከተ ፤ ልጆቹንም የልያ ልጆች ከልያ ፤ የራኄልን ልጆች ከራኄል ፤ የባላን ልጆች ከባላ ፤ የዘለፋን ልጆች ከዘለፋ አድርጎ ከፋፈላቸው ፤ ዘፍ. ፴፪ ፯ ። |
| ወረሰዮን ለዕቁባቲሁ ምስለ ደቂቆን ቅድመ ፤ ወለልያ ወለደቂቃ ድኅሬሆን ወለራኄልሰ ወለዮሴፍ ድኅሬሃ ። | ፪ | ዕቁባቶቹን ከልጆቻቸው ጋር በፊት ፤ ልያን ከልጆቿ ጋር ወደኋላ አደረጋቸው ፤ ራኄልንና ዮሴፍን ግን ከሁሉ በኋላ አደረጋቸው ። |
| ወውእቱሰ ሖረ ቅድሜሆሙ ወሰገደ ውስተ ምድር ስብዐ እስከ ይበጽሕ ኀበ እኁሁ ኤሳው ። | ፫ | እሱ ግን በፊት በፊታቸው ሄደ ፤ ከወንድሙ ከዔሳው እስኪደርስ ድረስ ግምባሩን ምድር እያስነካ ሰባት ጊዜ ሰገደ ። |
| ወአቅደመ ረዊጸ ዔሳው ወተቀበሎ ወሐቀፎ ክሳዶ ወሰዐሞ ወበከዩ ክልኤሆሙ ኅቡረ ። | ፬ | ዔሳውም በየው ጊዜ እየሮጠ ሄዶ አንገቱን አቅፎ ሳመው ፤ ሁለቱም ተያይዘው አለቀሱ ፤ ዘፍ. ፵፭ ፲፬ ። |
| ወሶበ ነጸረ ኤሳው ወርእዮን ለአንስት ወለደቂቆን ይቤሎ ምንትከ እሉ ፤ ወይቤሎ ያዕቆብ ደቂቅየ እሙንቱ ዘመሐሮ እግዚአብሔር ለገብርከ ። | ፭ | ዔሳውም ሁለቱ ሚስቶቹንና ልጆቻቸውን ባየ ጊዜ እነዚህ ምኖችህ ናቸው ፤ አለው ያዕቆብም እግዚአብሔር ለኔ ለአገልጋይህ የመጸወተኝ ልጆቼ ናቸው አለው ። |
| ወመጽአ ዕቁባቲሁ ወደቂቆን ምስሌሆን ወሰገዳ ። | ፮ | ዕቁባቶቹም ከልጆቻቸው ጋር መጥተው እጅ ነሡት ። |
| ወመጽአት ልያ ወደቂቃ ወሰገዱ ሎቱ ወእምዝ መጽአት ራኄል ወሰገደት ። | ፯ | ልያም ከልጆቿ ጋር መጥታ እጅ ነሣችው ፤ ከሁሉ በኋላም ራኄል መጥታ እጅ ነሣች ። |
| ወይቤሎ ኤሳው ለያዕቆብ ምንትከ ውእቱ ዝንቱ ኵሉ ትአይን ዘረከብኩ ፤ ወይቤሎ ያዕቆብ ለኤሳው ዘገበርኩ ለከ እግዚእ ከመ እርከብ ሞገሰ በቅድሜከ ። | ፰ | ዔሳውም ያዕቆብን ይህ ሁሉ ያገኘሁት ሠራዊት ምንህ ነው ፤ አለው ፤ ያዕቆብም ዔሳውን አቤቱ በፊትህ በለሟልነትን አገኝ ዘንድ ያደረግሁት ነው አለው ፤ ዘፍ. ፴፪ ፭ ። |
| ወይቤሎ ኤሳው ብየ እንስሳ ብዙኀ እኁየ ወይኩንከ ለከ ዘዚአከ ። | ፱ | ወንድሜ ለኔ ብዙ ከብት አለኝ ፤ ያንተ ገንዘብ ላንተ ይሁንልህ አለው ። |
| ወይቤሎ ያዕቆብ አኮ ከመዝ ለእመ ረከብኩ ሞገሰ በቅድሜከ ተመጠው አምኃየ እምእዴየ ፤ እስመ በእንተ | ፲ | ያዕቆብም እንዲህ አይደለም በፊትህ በለሟልነትን ካገኘሁ ያመጣሁትን እጅ መንሻዬን ተቀበለኝ አለው ። ስለ |

፲ ወሶበ አከ ዘጐንደይነ እምደገምነ ካዕበ ገቢአ ።

ባልዘገየን ኖሮ ሁለተኛ በተመለስን ነበር ።

፲፩ ወይቤሎሙ እስራኤል አቡሆሙ ለእመሰ ከመዝ ውእቱ ነገር ንሥኡ እምፍሬ ምድር ወደዩ ውስተ አሕስሊክሙ ወስዱ ለብእሲ አምኃ ርጢነ ወመዓረ ወዕጣነ ወማየ ልብን ወጠርቤንቶስ ወክርከዐ ።

አባታቸው እስራኤልም እንዲህ አላቸው ፥ ነገሩስ እንዲህ ከሆነ ከምድር ፍሬ ወስዳችሁ በሸልቻችሁ ቋጥሩ ፥ ለሰውየውም እጅ መንሻ መድኃኒት ማር ፥ ዕጣን ፥ ልብንጃ ለውዝገውዝ ሎሚ ውሰዱ ። ዘፍ፥ ፴፫ ፳፭ ።

፲፪ ወርቅክሙሰ ንሥኡ ካዕበቶ ምስሌክሙ ወዝንቱሂ ዘረከብክሙ በውስተ አሕስሊክሙ ወንሣእክምዎ በኢያአምሮ ከነ ዮጊ ።

ወርቃችሁን ዕጥፍ አድርጋችሁ ይህንም በዳውላችሁ ውስጥ ያገኛችሁትንም ያዙ ምናልባትም በለማወቅ ተደርጎ ይሆናል ። ዘፍ፥ ፵፪ ፳፭ ፥ ፳፯ ፴፭ ።

፲፫ ወንሥእዎ ለእኁክሙ ምስሌክሙ ወተንሥኡ ወረዱ ኀበ ብእሲ ።

ወንድማችሁንም ከናንተ ጋራ ውሰዱት ተነሥታችሁም ወደዚያ ሰው ውረዱ ።

፲፬ ወአምላኪየ የሀብክሙ ሞገሰ በኀበ ውእቱ ብእሲ ወያግብእ ለክሙ ለውእቱ እኁክሙ ወለብንያምኒ ወአንሰ ዳእሙ በከመ ኀጣእኩ ውሉደ ኃጣእኩ ።

ፈጣሪዬም በዚያ ሰው ዘንድ መወደድን ይስጣችሁ ፥ ያኛውንም ወንድማችሁን ብንያምንም ይመልስላችሁ እኔ ብቻ ልጆቼን እንዳጣሁ ቀረሁ ። ዘፍ፥ ፯ ፩ ።

፲፭ ወነሥኡ እሙንቱ እደው ውእተ አምኃ ወርቆሙኒ ካዕበተ ነሥኡ ምስሌሆሙ ወለብንያምኒ ነሥእዎ ወተንሥኡ ወወረዱ ብሔረ ግብጽ ወበጽሑ ቅድሜሁ ለዮሴፍ ወሰገዱ ሎቱ ።

እነዚያ ሰዎችም ያንን እጅ መንሻ ወርቃቸውንም በዕጥፍ ወስዱ ፥ ብንያምንም ይዘውት ተነሥተው ወደ ግብጽ አገር ወረዱ ፥ ከዮሴፍ ፊት ደርሰውም ሰገዱለት ።

፲፮ ወርእዮ ዮሴፍ ለብንያም ምስሌሆሙ ይቤሎ ለመጋቤ ቤቱ አብእሙ ለእሉ ሰብእ ውስተ ቤት ወጥባሕ ወአስተዳሉ ፥ እስመ ምስሌየ ይመስሑ እሉ እደው ፥ ወምስሌየ ይበልዑ መዓልተ ።

ዮሴፍም ብንያምን ከእነሱ ጋራ አየው የቤቱን ሹም እነዚህን ሰዎች ወደ ቤት አስገባቸው ፥ ፍሪዳ እረድ ፥ ምግብ አዘጋጅ ፥ እሊህ ሰዎች ከኔ ጋር ምሳ ይበላሉና ፥ በቀትር ጊዜም ከእኔ ጋር ይበላሉ አለው ። ዘፍ፥ ፵፫ ፲፱ ።

፲፯ ወገብረ ውእቱ ብእሲ በከመ ይቤሎ ዮሴፍ ወአብአሙ ለእሙንቱ እደው ውስተ ቤተ ዮሴፍ ።

ያም ሰው ዮሴፍ እንዳዘዘው አድርጎ እነዚያን ሰዎች ወደ ዮሴፍ ቤት አስገባቸው ።

፲፰ ወሶበ ርእዩ እሙንቱ እደው ከመ አብእምሙ ውስተ ቤተ ዮሴፍ ይቤሉ በእንተ ዝንቱ ወርቅ ዘገብአ ውስተ አሕስሊነ ዘቀዲሙ ይወስዱነ ከመ ይኰንኑነ ወይቅንዩነ ወይንሥኡነ እንስሳነ ።

እነዚያም ሰዎች ወደ ዮሴፍ ቤት እንዳስገቧቸው በዩ ጊዜ ቀድሞ በዳውላችን ስለተመለሰው ስለዚህ ወርቅ አስጨንቀው ሊገዙን ከብቶቻችንንም ሊወስዱብን ይሆናል አሉ ።

፲፱ ወቀርቡ ኀበ ውእቱ ብእሲ ዘላዕለ ቤተ ዮሴፍ ወተናገርዎ በኆኅተ ቤቱ ።

በዮሴፍ ቤት ላይ ወደ ተሾመው ወደዚያ ሰው ቀርበው በቤቱ በራፍ ላይ አነጋገሩት ።

፳ ወይቤልዎ ናስተበቍዐከ እግዚእ ቀዲሙ ወረድነ ንሣየጥ እክለ ።

እንዲህም አሉት አቤቱ እንግልድሃለን ቀድሞ እኽል ልንሸምት ወርደን ነበር ። ዘፍ፥ ፵፪ ፫ - ፲ ።

፳፩ ወኮነ ሶበ በጻሕነ ለኀዲር ወፈታሕነ አሕሳሊነ ረከብነ ወርቀ ውስተ አሕስሊነ ዘዘዚአነ ፥ ወይእዜኒ ወርቀሰ አግባእነ ምስሌነ በመድሎቱ ።

ሸምተን ከምናድርበት ቦታ በደረስን ጊዜ እንዲህ ሆነ አይበታችንን ፈትተን የየራሳችንን ወርቅ በአይበታችን ውስጥ አገኘነው አሁንም ወርቁን በሚዛኑ ከኛ ጋር መልሰን አምጥተናል ። ዘፍ፥ ፵፪ ፳፯ ።

፳፪ ወካልአኒ ወርቀ አምጻእነ በዘንሣየጥ እክለ ወኢያአመርነ መኑ ወደዮ ለውእቱ ወርቅ ውስተ አሕሳሊነ ።

እኽልን የምንሸምትበት ሌላም ወርቅ አምጥተናል ፥ ግን ያንን ወርቅ በአይበታችን ማን እንደጨመረው አላወቅንም ።

፳፫ ወይቤሎሙ ውእቱ ብእሲ ሐሰ ለክሙ ኢትፍርሁ አምላክክሙ ወአምላከ አበዊክሙ ወሀበክሙ መድፍነ በውስተ አሕሳሊክሙ ወርቅክሙሰ ሠሚርየ ነሣእኩ ፥ ወአውጽአ ለስምዖንሂ ኀቤሆሙ ።

ያም ሰው አይዟችሁ አትፍሩ ፥ ፈጣሪያችሁ የአባቶቻችሁም ፈጣሪ የተቀበረ ወርቅን በዳውላችሁ ሰጥቶአችኋል ወርቃችሁንስ ወድጄ ተቀብያለሁ አላቸው ፥ ስምዖንንም እነሱ ወዳሉበት አወጣው ።

፳፬ ወአምጽአ ማየ ለእገሪሆሙ ወወሀበ እክለ ለአእዱጊሆሙ ።

ለእግራቸውም ውኃ አመጣ ፥ ለአህዮቻቸውም ገፈራ ሰጠ ። ዘፍ፥ ፲፰ ፬ ፥ ፲፱ ፪ ፥ ፳፬ ፴፪ ።

፳፭ ወአስተዳለዉ አምኃሆሙ እስከ ይበውእ ዮሴፍ መዓልተ እስመ ሰምዑ ከመ በሀየ ይመስሕ ።

ዮሴፍም በቀትር ጊዜ እስኪገባ ድረስ እጅ መንሻቸውን አዘጋጁ ፥ በዚያ ምሳ እንደሚያደርግ ሰምተዋልና ።

፳፮ ወሶበ መጽአ ዮሴፍ ውስተ ቤቱ አምጽኡ ሎቱ አምኃሁ ዘውስተ እደዊሆሙ ውስተ ቤት ፥ ወሰገዱ ሎቱ በገጾሙ ውስተ ምድር ።

ዮሴፍም ወደ ቤቱ በመጣ ጊዜ በእጃቸው ያለውን እጅ መንሻ በቤት ውስጥ አቀረቡለት ፥ በግንባራቸውም በምድር ላይ ወድቀው ሰገዱለት ።

፳፯ ወተስእሎሙ ዜናሆሙ ወይቤሎሙ ዳኅንኑ ዝኩ አቡ
ክሙ አረጋዊ ዘትቤሉኒ ዓዲሁ ሕያውኑ ውእቱ ።

፳፰ ወይቤልዎ ዳኅን ገብርከ አቡነ አረጋዊ ወዓዲሁ ሕያ
ው ውእቱ ወይቤ ዮሴፍ ቡሩክ ውእቱ ብእሲሁ ለእግዚ
አብሔር ወአትሐቱ ርእሶሙ ወሰገዱ ሎቱ ።

፳፱ ወሰበ ነጸሮ ዮሴፍ ወርእዮ ለብንያም እኁሁ ወልደ
እሙ ይቤሎሙ ዝኑ ውእቱ እኁክሙ ዘይንእስ ዘትቤሉኒ
ናመጽኦ ኀቤክ፣ ወይቤልዎ እወ፣ ወይቤሎ ዮሴፍ እግዚ
አብሔር ይሣሀልከ ወልድየ ።

፴ ወተሀውከ ዮሴፍ አማዑቲሁ ወፈቀደ ይብኪ ወቦአ
ውስተ ቤቱ ወበከየ ።

፴፩ ወተሐፅበ ገጾ ወወፅአ ተዐጊሦ ወይቤ አቅርቡ ለነ
ኅብስተ ።

፴፪ ወአቅረቡ ሎሙ እንተ በሕቲቶሙ ወሎቱኒ እንተ
ብሕቲቱ፣ ወለሰብአ ግብጽ እለ ይመስሑ ምስሌሁ እንተ
በሕቲቶሙ እስመ ኢይክሉ ሰብአ ግብጽ በሊዐ እክል
ምስለ ዕብራውያን እስመ ያስቆርርዎሙ ሰብአ ግብጽ ለኵ
ሎሙ ኖሎት ።

፴፫ ወነበረ ቀድሜሆሙ በኵሮሙ ዘይልህቅ፣ ወዘይንእስኒ
በበናእሱ፣ ወነበሩ አሐዱ አሐዱ ምስለ ካልኡ ።

፴፬ ወነሥኡ ክፍሎሙ በኀቤሁ ዘዘዚአሆሙ፣ ወዐብየ ክ
ፍሉ ለብንያም እምክፍሎሙ ኃምስተ እደ ወበልዑ ወሰ
ትዩ ወሰክሩ ምስሌሁ ።

ምዕራፍ ፵፬ ።

፩ ወአዘዘ ዮሴፍ ለመጋቢሁ ወይቤሎ ምላእ ሎሙ አሕ
ሳኪሆሙ ለእሉ እደው መጠነ ይክሉ ፆዊረ፣ ወደይ ለለአ
ሐዱ ወርቆሙ ውስተ አሕሳኪሆሙ ።

፪ ወኮራየ ዘብሩር ደይ ውስተ ሐሰሉ ለዘይንእስ ወሤ
ጠ እክሉሂ ደይ፣ ወገብረ በከመ አዘዘ ዮሴፍ ።

፫ ወሰበ ጎህ ጽባሕ ፈነውሙ ለእሙንቱ እደው ምስለ
እንስሳሆሙ ።

፬ ወሰበ ወፅኡ እሙንቱ እደው ዘእንበለ ይርኅቁ እም
ሀገር ነዋኀ ይቤሎ ዮሴፍ ለመጋቤ ቤቱ ተንሥእ ዴግኖሙ
ወትልዎሙ ለእሉ እደው ወአኀዞሙ ወበሎሙ እፎ እኪ
ተ ትፈድዩኒ ህየንተ ሠናይ ።

፭ ለምንት ትሰርቁኒ ገይበ ብሩር ዘቦቱ ይሰቲ እግዚእየ
እኩየ ገበርክሙ በሎሙ ።

፮ ወሐረ ወረከቦሙ ወይቤሎሙ ለምንት ትገብሩ ከመ
ዝ ወትፈድዩኒ እኪተ ህየንተ ሠናይ ዘገበርኩ ለክሙ ወት
ሰርቁኒ ገይበ ብሩር ዘእግዚእየ ።

፯ ወይቤልዎ ለምንት ትብል ከመዝ እግዚእነ ሐሰ ሎሙ
ለአግብርቲከ ኢይገብርዎ ለዝንቱ ነገር ።

፰ ወርቀ ጥቀ ዘረከብነ በውስተ አሕሳኪነ አግባእነ ኀቤ
ከ እምድረ ከነዓን ወእፎኬ ንሰርቅ እምቤትከ ወርቀ አው
ብሩረ ።

አለ ገና ከጕልበት ነው ያላችሁኝ ያ ሽማግሌ አባታ
ችሁ ደኅና ነውን፤ ገና ከጕልበት ነውን፤ ብሎ ደኅንነታ
ቸውን ጠየቃቸው ። ፩ ሳሙ፣ ፲፯ ፲፤ ።

አገልጋይህ ሽማግሌ አባታችን ደኅና ነው፣ ከጕልበ
ትም ነው አሉት፣ ዮሴፍም ሰውየው ለእግዚአብሔር ደግ
ፍጥረት ነው አለ፣ ራሳቸውንም ዝቅ አድርገው ሰገዱለት።

ዮሴፍም የእናቱን ልጅ ወንድሙ ብንያምን አሻግሮ
በየው ጊዜ ወዳንተ እናመጣዋለን ያላችሁኝ ታናሽ ወን
ድማችሁ ይህ ነውን፤ አላቸው፣ አዎን አሉት፣ ዮሴፍም
ልጄ እግዚአብሔር ይቅር ይበልህ አለው ። ዘፍ፣ ፴፭ ፲፰።

ዮሴፍም አንጀቱ ታወከ ሊያለቅስም ፈለገ ወደ እል
ፍኙም ገብቶ አለቀሰ ። ፩ ነገ፣ ፫ ፳፯ ። ሆሴ፣ ፲፩ ፰ ።

እንባውን ታግሦ ፊቱን ታጥቦ ወጣና እንጀራ አቅር
ቡልን አለ ። ዘፍ፣ ፵፫ ፩ ።

ለነሱም ለብቻቸው አቀረቡላቸው፣ ለሱም ለብቻው
ከርሱም ጋር ምሳ ለሚበሉ ለግብጽ ሰዎችም ለብቻቸው፣
የግብጽ ሰዎች ዘላኖችን ሁሉ ስለሚጸየፉዋቸው ግብጻው
ያን ከዕብራውያን ጋራ አብሮ መብላትን አይችሉምና ።
ዘፍ፣ ፵፯ ፵፬ ። ዘፀ፣ ፰ ፯ - ፯ ።

ታላቅ ወንድማቸውም በፊታቸው ተቀመጠ፣ ታናሹም
እንደታናሽነቱ ተቀመጠ፣ አንዱም ከንዱ ጋራ ተቀመጡ ።

የየራሳቸውን ፈንታቸውን ከሱ ዘንድ ተቀበሉ፣ የብን
ያም ፈንታ ግን ከእነሱ ፈንታ አምስት እጅ በለጠ፣ ከሱም
ጋራ አብዝተው በልተው ጠጥተው ደስ አላቸው ።

ምዕራፍ ፵፬ ።

ዮሴፍ አዛዥን ጠርቶ እንዲህ አለው፤ ለነዚህ ሰዎች
አይበታቸው የሚችሉትን ያህል ሙላላቸውን የያንዱንም
ወርቃቸውን የያንዳንዱ በየአይበታቸው አድርግላቸው ።

የብር ጽዋዬንም በታናሹ አይበት አድርግ የእኽሉንም
ዋጋ አብረህ አድርግ፣ እሱም ዮሴፍ እንዳዘዘው አደረገ ።

ጎህም በቀደደ ጊዜ እነዚያን ሰዎች ከከብቶቻቸው
ጋራ ሸኝቶ ሰደዳቸው ።

እነሱም በወጡ ጊዜ ከከተማ በጣም ሳይርቁ ዮሴፍ
አዛዡን ጠርቶ እንዲህ አለው፤ ተነሥተህ እነዚያን ሰዎች
ተከትለህ ያዛቸው እንዲህም በላቸው ስለ በጎ ነገር ፈንታ
እንዴት ክፉ ነገር ትከፍሉኛላችሁ፤

ጌታዬ የሚጠጣበትን የብሩን ጽዋ ለምን ሰረቃችሁኝ፤
ክፉ ነገር አደረጋችሁ በላቸው ። ዘፍ፣ ፵፬ ፲፭ ።

ሂዶም በገኛቸው ጊዜ ለምን እንደዚህ ታደርጋላችሁ፤
በጎ ስለ አደረግሁላችሁስ ፈንታ ለምን ክፉ ነገር ትከፍሉ
ኛላችሁ፤ የጌታዬንስ የብሩን ጽዋ ለምን ትሠርቁኛላችሁ፤
አላቸው ።

እነሱም እንዲህ አሉት ጌታችን ለምን እንዲህ ትላ
ለህ፤ ለኛ ለአገልጋዮችህ አገባባቸው አይደለም ይህንን
ነገር አያደርጉትም ።

በአይበታችን ያገኘነውን ወርቅን እንኳ ከከነዓን ምድ
ር መልሰን አመጣንልህ ከቤትህ ወርቅ ወይስ ብር እን
ዴት እንሰርቃለን ። ዘፍ፣ ፵፫ ፳፩ ።

ይእዜኒ በኀበ ዘረከብከ ክራከ እምአግብርቲከ ለይ ፱
ሙት ወንሕነኒ ንኩን አግብርተ ለእግዚእከ ።
ወይቤሎሙ ይእዜኒ ይኩን በከመ ትቤሉኒ ዘኀቤሁ ፲
ተረከበ ውእቱ ገይብ ይኩነኒ ገብረ፣ ወአንትሙሰ አንጹሕ
ክሙ ርእሰክሙ ።
ወአውረዱ አሕሳሊሆሙ ውበተ ምድር ፍጡነ ። ፲፩
ወአኀዘ ይፍትሒ እምነ ዘይልህቅ እስከ ዘይንእስ፣ ፲፪
ወረከበ ውእተ ገይበ በውስተ ሐስለ ብንያም ።

ወሰጠጡ አልባሲሆሙ ወጸዐኑ አሕስሊሆሙ ዲበ ፲፫
አእዱጊሆሙ ወገብኡ ውስተ ሀገር ።
ወበኡ ኀበ ቤተ ዮሴፍ እንዘ ሀሉ ውእቱ ህየ ወወድቁ ፲፬
ውስተ ምድር በገጾሙ ።
ወይቤሎሙ ዮሴፍ ምንትኑ ዝንቱ ዘገበርክሙ ። ፲፭

ወይቤ ይሁዳ ምንተ ናወሥእ ለእግዚእነ ወምንተ ን ፲፮
ብል ወበምንት ንነጽሕ ዘእግዚአብሔር አግብአ ለዐመፃነ
ላዕሌነ ወበሕቱ ናሁ ክነ አግብርቲሁ ለእግዚእነ ንሕነሂ
ወዝንቱሂ ዘተረክበ በኀቤሁ ገይብ ።
ወይቤ ዮሴፍ ሐሰ ሊተ እስከ እገብሮ ለዝንቱ ነገር ፲፯
አላ ውእቱ ብእሲ ዘበላዕሌሁ ተረክበ ክራይ ውእቱ ይኩ
ነኒ ገብረ አንትሙሰ ሑሩ ወግብኡ ኀበ አቡክሙ በዳኅን።
ወቀርበ ይሁዳ ኀቤሁ ወይቤ ብቍዐኒ እግዚእ ወእብ ፲፰
ሐኒ እንብብ ቅድሜከ እግዚእየ ኢትትመዓዖ ለገብርከ
እስመ አንተ እምድኅረ ፈርዖን እግዚእ ።
አንተ ተስእልከሙ ለአግብርቲከ ወትቤሎሙ ቦኑ ዘብ ፲፱
ክሙ አብ አው እኁ ።
ወንቤለከ እግዚእ ብነ አብ አረጋዊ ወቦ ወልድ ንኡስ ፳
ዘበርሥዓኑ ወለዶ ወእሁኁሰ ሎቱ ሞተ ወውእቱ ባሕቲቱ
ተርፈ ለእሙ ወያፈቅሮ አቡሁ ።
ወትቤሎሙ ለአግብርቲከ አምጽእዎ ኀቤየ ወእዐቅቦ። ፳፩

ወንቤለከ ኢይክል ኀዲገ አቡሁ ውእቱ ሕፃን ወእ ፳፪
መሰ ኀደጎ ይመውት ።
ወአንተሰ ባሕቱ ትቤሎሙ ለአግብርቲከ ለእመ ኢያ ፳፫
ምጻእክምዎ ለእኁክሙ ዘይንእስ ኢትሬእዩ ገጽየ ዳግመ።
ወኮነ ሶበ ዐረግነ ኀበ አቡነ ገብርከ ዜነውናሁ ዘንተ ፳፬
ዘትቤለነ እግዚእነ ።
ወይቤለነ አቡነ ሑሩ ካዕበ ተሣየጡ ለነ ኀዳጠ እክለ። ፳፭

ወንቤሎ ንሕነሰ ኢንክል ሐዊረ ለእመ እኁነ ዘይንእስ ፳፮
ኢመጽአ ምስሌነ እስመ ኢንክል ርእየ ገጹ ለውእቱ ብእ
ሲ እመ ኢሀሎ እኁነ ዘይንእስ ምስሌነ ።
ወይቤለነ ገብርከ አቡነ ተአምሩ ለሊክሙ ከመ ክል ፳፯
ኤተ ወለደት ሊተ ይእቲ ብእሲት ።
ወአሐዱሰ ወፅአ እምኀቤየ ወትቤሉኒ አርዌ በልዖ ፳፰
ወኢርኢክዎ እንከ ዳግመ እስከ ይእዜ ።
ወለእመ ነሣእክምዎ ለዝኒ እምቅድመ ገጽየ ወእም ፳፱
ከመ ደወየ በፍኖት ታወርድዎ ለርስዓንየ በኀዘን ውስተ
መቃብር ።

አሁንም ከአገልጋዮችህ ጽዋህን ያገኘህበት ሰው ይ
ሙት እኛም ለጌታህ ባሮች እንሁን አሉት ።
አሁንም እንዳላችሁኝ ያ ጽዋ የተገኘበት ሰው
ባርያ ይሁነኝ፣ እናንተ ግን ራሳችሁን ነፃ አድርጋችኋል
አላቸው ።
አይበታቸውንም ፈጥነው ወደ ምድር አወረዱው ።
ከታላቁ ወንድማቸው ጀምረው እስከ ታናሽ ወንድማ
ቸው ድረስ ይፈቱ ጀመሩ፣ (እሱም) ጽዋውን በብንያም
አይበት አገኘ ።
(እነሱም) ልብሳቸውን ቀደዱ፣ አይበታቸውም በአህ
ዮቻቸውን ጭነው ወደ ከተማ ተመለሱ ።
እሱ ከዚያ ሳለም ወደ ዮሴፍ ቤት ገቡ፣ በምድርም
ወድቀው ሰገዱለት ። ዘፍ፥ ፴፯ ፯ ፱ - ፲ ።
ዮሴፍም ይህ ያደረጋችሁት ነገር ምንድር ነው፤ አላ
ቸው ። ዘፍ፥ ፵፬ ፭ ።
ይሁዳም ለጌታችን ምን እንመልስለታለን ምንስ እን
ላለን እግዘ አብሔር ፍዳችንን በኛ ላይ ከሡጣው በምን
እንነጻለን፣ ነገር ግን እኛም ጽዋው ከሱ ዘንድ የተገኘበት
እሱም እነሆ ለጌታችን ባሮች ሆን አለ ።
ዮሴፍም ይህን ነገር አደርገው ዘንድ አይገባኝም፣ ጽ
ዋዬ የተገኘበት ያ ሰው ብቻ ባርያዬ ይሁነኝ እንጂ እና
ንተስ ተመልሳችሁ ወደ አባታችሁ በደኅና ሂዱ አላቸው።
ይሁዳም ወደሱ ቀርቦ አቤቱ በጅ በለኝ ጌታዬ ! በፊ
ትህ እንድናገር ፍቀድልኝ ባርያህን አትቆጣው አንተ ከፈ
ርዖን ቀጥሎ ገዥ ነህና ። ዘፀ፥ ፴፪ ፳፪ ።
አባት ወይም ወንድም አላችሁን፤ ብለህ አንተ ባሮ
ችን ጠየቅኸን ።
አቤቱ፣ ሽማግሌ አባት አለን በእርጅናው ጊዜ የወለ
ደው ትንሽ ልጅም አለው፣ ወንድሙ ግን ሙቶ ለናቱ
እሱ ብቻ ቀርቷል፣ አባቱም ይወደዋል አልንህ ።
ባሮችህን ወደኔ አምጡት፣ እኔም እከባከበዋለሁ አል
ከቸው ። ዘፍ፥ ፵ ፲፭ - ፳ ።
(እኛም) ያ ልጅ አባቱን መተው አይችልም ቢተወ
ውም ይሞታል አልንህ ። ዘፍ፥ ፵፬ ፴፩ ።
አንተ ግን ባሮችህን ታናሽ ወንድማችሁን ካላመጣ
ችሁት ዳግመኛ ፊቴን አታዩም አልከን ።
ወደ ባርያህ ወደ አባታችን በተመለስንም ጊዜ
አንተ ጌታችን ያዘዝከንን ነገርነው ።
አባታችንም ዳግመኛ ሂዱችሁ ጥቂት እኽል ሸምቱ
ልን አለን ። ዘፍ፥ ፵፫ ፩ ።
እኛም ታናሽ ወንድማችን ከኛ ጋራ ካልሄደ መሄድን
አንችልም፣ ወንድማችን ከኛ ጋራ ከሌለ የዚያን ሰው ፊት
ማየት አንችልምና አልነው ።
ባርያህ አባታችንም እንዲህ አለን ያች ሴት ሁለት
ልጆች እንደወለደችልኝ እናንተ ታውቃላችሁ ።
አንዱ ግን ከኔ ተለይቶ ሂዶ አውሬ በላው አላችሁኝ
እንግዲህ እስከሁን ድረስ መልሼ አላየሁትም ።
ይህንንም ከፊቴ ወስዳችሁት በመንገድ ታሞም (ቢ
ሞት) ያረጀ ሰውነቴን በኀዘን ወደ መቃብር ታወርዱ
ታላችሁ አለን ።

፴ ወይእዜኒ ለእመ ሖርነ ኀበ ገብርከ አቡነ ወኢሀሎ
ምስሌነ ዝንቱ ሕፃን ይመውት ወናወርዶ ውስተ መቃብር
በጻዕር ለርስዓኒሁ ለገብርከ አቡነ ።
፴፩ እስመ ገብርከ ተሐበየ ለዝንቱ ሕፃን እምአቡሁ ወይ
ቤሎ ለእመ ኢያገባእክዎ ኀቤከ ወኢያቀምክዎ ቅድሜከ
ጊጉየ ለእቡን ሳዕሌሁ አበ በኵሉ መዋዕለ ሕይወትየ ።
፴፪ ወይእዜኒ እክውንከ ገብረ ህየንተ ዝ ሕፃን፣ ወእነብር
ኀቤከ እግዚአ ወሕፃንሰ ይሑር ምስለ አኀዊሁ ።
፴፫ እስመ ኢይክል አነ ሐዊረ ኀበ አቡነ ለእመ ኢሀሎ
ዝንቱ ሕፃን ኀቤነ ከመ ኢይርአይ እኪተ እንተ ትረክቦ
ለአቡነ ።

ምዕራፍ ፵፭።

፩ ወሶበ ስእነ ዮሴፍ ተዐግሦ እንዘ ኵሉ ይቀውም ቅድ
ሜሁ፤ ይቤ ዮሴፍ ያሰስሉ ኵሎ ሰብአ እምቅድሜሁ ወአ
ውፅኡ ኵሎ ሰብአ እምቅድሜሁ ወአልቦ ዘተርፈ ህየ ኀበ
ዮሴፍ ሶበ ይትአመር ምስለ አኀዊሁ ።
፪ ወጸርሐ በዐቢይ ቃል ወበከየ፣ ወሰምዑ ኵሉ ሰብአ
ግብጽ ወተሰምዐ በቤተ ፈርዖንሂ ።
፫ ወይቤሎሙ አነ ውእቱ ዮሴፍ እኁክሙ፣ ሕያውኑ
ዓዲሁ ውእቱ አቡየ ወኢክህሉ አውሥኦቶ እስመ ደንገፁ ።

፬ ወይቤሎሙ ዮሴፍ ለአኀዊሁ ቅረቡ ኀቤየ፣ ወቀርቡ
ኀቤሁ ወይቤሎሙ አነ ውእቱ ዮሴፍ እኁክሙ ዘሤጥክ
ሙኒ ኀበ ብሔረ ግብጽ ።
፭ ወይእዜኒ ኢትፍርሁ እስመ ሤጥክሙኒ ዝየ እስመ
ለሕይወት ፈነወኒ እግዚአብሔር ቅድሜክሙ ።
፮ እስመ ናሁ ክልኤቱ ዓመት ኀለፈ ዘረኃብ ላዕለ ምድር
ወዓዲ ሀሎ ኀምስቱ ዓመት ወአልቦ ዘየሐርስ ወዘይዘርእ ።
፯ ወፈነወኒ እግዚአብሔር ቅድሜክሙ ከመ ትሕየዉ
ወትትርፉ ዲበ ምድር ከመ እሴሲክሙ ።
፰ ወይእዜኒ አኮ አንትሙ ዘፈነውክሙኒ ዳእሙ እግዚ
አብሔር ፈነወኒ ወረሰየኒ ወልዶ ለፈርዖን፣ ወእግዚአ
ለኵሉ ቤቱ፣ ወመልአከ ለኵሉ ግብጽ ።
፱ ወይእዜኒ ሑሩ ንግርዎ ለአቡየ ፍጡነ ወበልዎ ከመ
ዝ ይቤ ወልድከ ዮሴፍ፣ እግዚአብሔር ረሰየኒ እግዚአ
ለኵሉ ብሔረ ግብጽ፣ ወረድ እንከ ፍጡነ ወኢትንበር ህየ።

፲ ወተኀደር ውስተ ምድረ ጌሴም ዘዓረብ ወትሄሉ ቅሩ
ብየ አንተ ወደቂቅከ ወአበግዒከ ወአልሕምቲከ ወኵሉ
ዘብከ ።
፲፩ ወእሴስየከ በህየ፣ እስመ ዓዲ ሀሎ ኀምስቱ ዓመት ዘረ
ኃብ ከመ ኢትሙት አንተ ወኵሉ ቤትከ ወኵሉ ጥሪትከ።

፲፪ ወናሁ ትሬእዩ በአዕይንቲክሙ ወብንያምኒ እኁየ
ርእየ በአዕይንቲሁ ከመ ለልየ ተናገርኩክሙ በአፉየ ።
፲፫ ወዜንውዎ ለአቡየ ኵሎ ክብርየ ዘብሔረ ግብጽ ወኵ
ሎ ዘርኢክሙ በአዕይንቲክሙ ወአፍጥኑ አምጽኦቶ ለአ
ቡየ ዝየ ።

፴ አሁንም እኛ ወደ ባርያህ ወደ አባታችን ብንሄድ
ብላቴናውም ከእኛ ጋራ ከሌለ ይሞታል ያረጀ ሰውነቱ
ንም በኃዘን ወደ መቃብር እናወርደዋለን ።
፴፩ እኔ ባርያህ ብላቴናውን ከባቱ ዋስ ሆኜ አምጥቼ
ዋለሁና ወደ አንተ መልሼ አምጥቼ ከፊትህም ባላቆመው
በሰዘመኔ ሁሉ አንተን የበደልሁ ልሁን ብዬ ዋስሁና ።
፴፪ አሁንም እኔ ስለዚህ ሕፃን ፈንታ ባርያህ እሆንሃለሁ
አቤቱ ከንተ ዘንድም እቀመጣለሁ ብላቴናው ግን ከወንድ
ሞቹ ጋር ይሂድ ። ዘፍ፡ ፵፬ ፴ ።
፴፫ ይህ ብላቴና ከኛ ጋራ ከሌለ አባታችንን የሚያገኘውን
መከራ እንዳላይ ወደ አባቴን መሄድ አልችልምና ።

ምዕራፍ ፵፭።

፩ ዮሴፍም ሰው ሁሉ በፊቱ ቁሞ ሳለ መቻል በተሳነው
ጊዜ ሰውን ሁሉ ከፊቱ ያስወጡ ዘንድ አዘዘ፤ ከፊቱም
ሰውን ሁሉ አስወጡ፤ ከወንድሞቹም ጋራ በሚተዋወቅ
በት ጊዜ ከዚያ ከዮሴፍ ዘንድ የቀረ ሰው አልነበረም ።
፪ ቃሉንም አሰምቶ አለቀሰ፤ የግብጽ ሰዎችም ሁሉ
ሰሙ፤ በፈርዖን ቤትም (ጩኸቱ) ተሰማ ። ዘኍ፡ ፲፬ ፩ ።
፫ እሱም እኔ ወንድማችሁ ዮሴፍ ነኝ፤ አባቴ ገና በሕ
ይወት አለን፤ አላቸው፤ ደንግጠዋልና ሊመልሱለት አል
ቻሉም ። ኢዮብ ፬ ፭ ። ፳፫ ፲፭ ። ግብ፡ ሐዋ፡ ፯ ፲፫ ።
፬ ዮሴፍም ወንድሞቹን ወደኔ ቅረቡ አላቸው፤ ወደሱም
ቀረቡ እንዲህም አላቸው፤ ወደ ግብጽ የሸጣችሁኝ እኔ
ወንድማችሁ ዮሴፍ ነኝ ።
፭ አሁንም ወደዚህ ስለሸጣችሁኝ አትፍሩ እግዚአብሔር
ከናንተ አስቀድሞ ለሕይወት ሰዶኛልና ። መዝ፡ ፻፭ ፲፮ ፲፯ ።
፮ እነሆ በምድር ላይ ሁለቱ የራብ ዘመን አልፎአል ገና
አምስት ዓመት አለ፤ የሚያርስም የሚዘራም የለም ።
፯ እንድትድኑ በምድር ላይም እንድትተርፉ እመግብ
ችሁ ዘንድ እግዚአብሔር ከእናንተ አስቀድሞ ልኮኛልና ።
፰ አሁንም እግዚአብሔር ልኮ የፈርዖን ልጅ ለቤቱም
ሁሉ ገዥ ለግብጽም ሁሉ አለቃ አደረገኝ እንጂ እናንተ
የላካችሁኝ አይደለም ። ዘፍ፡ ፵፭ ፳፯ ። ፵፩ ፵፫ ።
፱ አሁንም ፈጥናችሁ ሂዳችሁ ለአባቴ ንገሩት፤ እንዲ
ህም በሉት፤ ልጅህ ዮሴፍ እንዲህ ብሏል፤ እግዚአብሔር
ለግብጽ አገር ሁሉ ገዥ አድርጎኛል እንግዲህ ፈጥነህ ው
ረድ እዚያም አትቀመጥ ።
፲ በምዕራብ በኩል ባለ በጌሴም ምድር ትቀመጣለህ
በአጠገቤ ትኖራለህ አንተም ልጆችህም በጎችህም ላሞች
ህም የአንተም ያለህም ሁሉ ።
፲፩ በዚያም እመግብሃለሁ ገና አምስት ዓመት የረኃብ
ዘመን አለና አንተ እንዳትሞት ልጆችህም ገንዘብህም
ሁሉ እንዳይሞቱ ። ምሳ፡ ፳ ፲፫ ።
፲፪ እኔ በቃሌ እንደተናገርኋችሁ እነሆ በዓይኖቻችሁ ታያ
ላችሁ ወንድሜ ብንያምም ባይኖቹ አይቷል ።
፲፫ በግብጽ አገር ያለ ጌትነቴን ባይናችሁም ያያችሁትን
ሁሉ ላባቴ ንገሩት፤ አባቴን ፈጥናችሁ ወደዚህ አምጡት
አላቸው ። ግብ፡ ሐዋ፡ ፯ ፲፬ ።

፲፬ ወሐቀፎ ክሳዶ ለብንያም እኁሁ ወበከየ ላዕሌሁ ወብ
ንያምኒ በከየ ላዕለ ክሳዱ ።
፲፭ ወሰዓሞሙ ለኵሎሙ ወበከየ ላዕሌሆሙ ፤ ወእምድ
ኅረዝ ተናገርዎ አኀዊሁ ለዮሴፍ ።
፲፮ ወተሰምዐ ነገሩ በቤተ ፈርዖን ፡ ወይቤልዎ አኀዊሁ
ለዮሴፍ መጽኡ ወተፈሥሐ ፈርዖን ወኵሉ ሰብኡ ።
፲፯ ወይቤሎ ፈርዖን ለዮሴፍ በሎሙ ለአኀዊከ ምልኡ
ንዋያቲክሙ ወሑሩ ብሔረ ከነአን ።
፲፰ ወንሥእዎ ለአቡክሙ ወለኵሉ ንዋይክሙ ወንዑ
ኀቤየ ወእሁበክሙ እምኵሉ በረከተ ግብጽ ወትበልዑ
አንጕዓ ለምድር ።
፲፱ ወአንተሰ ከመዝ አዝዞሙ ለአኀዊከ ይንሥኡ ሎሙ
ሠረገላተ ዘብሔረ ግብጽ ለደቂቆሙ ወለአዋልዲሆሙ
ወለአንስትያሆሙ ወይንሥእዎ ለአቡሆሙ ወያምጽእዎ ።
፳ ወኢይምሀኩ ቈሳቍሰሙ ወዘርእየት ዐይኖሙ እስመ
ኵሉ በረከተ ግብጽ ሎሙ ውእቱ ።
፳፩ ወገብሩ ከማሁ ደቂቀ እስራኤል በከመ ይቤሎሙ ፡
ወወሀቦሙ ሠረገላተ ዮሴፍ በከመ ይቤሎ ፈርዖን ንጉሠ
ግብጽ ፡ ወወሀቦሙ ስንቆሙ ለፍኖት ።
፳፪ ወወሀቦሙ ዐራዘ በበክልኤቱ፡ ወለብንያምሰ ወሀበ
ሠለስተ ምእተ ዲናረ ወኀምስተ ዐራዘ በዘያስተባሪ ወለ
አቡሆሙኒ ከማሁ ።
፳፫ ወፈነወ ዐሠርተ አእዱገ ዘይፀውሩ እምኵሉ በረከተ
ግብጽ፡ ወዐሠርተ አብቅለ እለ ይፀውሩ ስንቀ ለአቡሁ
በፍኖት ።
፳፬ ወፈነዎሙ ለአኀዊሁ ወይቤሎሙ አልበ ዘትትጋአዙ
በፍኖት ።
፳፭ ወወዕኡ እምብሔረ ግብጽ ወሖሩ ወበጽሑ ምድረ
ከነአን ኀበ አቡሆሙ ።
፳፮ ወዜነውዎ ወይቤልዎ ሕያው ዮሴፍ ወልድከ ወው
እቱ መልአከ ለብሔረ ግብጽ ወሰኵሉ ደወላ ወደንገፀ
ልቡ ወኢአምኖሙ ።
፳፯ ወነገርዎ ኵሎ ዘይቤሎሙ ዮሴፍ ወኵሎ ዘተናገሮሙ
ወሰበ ርእየ ሠረገላተ ዘፈነወ ዮሴፍ ሐይወ ልቡ ወተፈ
ሥሐ ነፍሱ ለያዕቆብ አቡሆሙ ።
፳፰ ወይቤ ያዕቆብ ዐቢይ ውእቱ ሊተ ዝንቱ እመ ዓዲሁ
ሕያው ውእቱ ዮሴፍ ወልድየ አሐውር እርእዮ ዘእን
በለ እሙት ።

ምዕራፍ ፵፮ ።

፩ ወተንሥአ እስራኤል ምስለ ኵሉ ንዋዩ ወበጽሐ
ኀበ ዐዘቅተ መሐላ ወሦዐ መሥዋዕተ ለአምላከ ይስሐቅ
አቡሁ ።
፪ ወይቤሎ እግዚአብሔር በሕልም ለእስራኤል ያዕቆብ
ያዕቆብ„! ወይቤ ምንት ውእቱ ።
፫ ወይቤሎ አነ ውእቱ አምላከ አበዊከ ኢትፍራህ
ወሪደ ኀበ ብሔረ ግብጽ እስመ ሕዝበ ዐቢየ እሬስየከ
በህየ ።
፬ ወአነ እወርድ ምስሌከ ውስተ ብሔረ ግብጽ ወእኄሉ

የወንድሙ የብንያምን አንገት አቅፎ አድርጎ በርሱ
ላይ አለቀሰ ብንያምም አንገቱን አቅፎ አለቀሰ ።
ሁሉንም ሳማቸው በነርሱም ላይ አለቀሰ ፡ ከዚህም
በኋላ ወንድሞቹ ዮሴፍን አጫወቱት ።
ነገሩም በፈርዖን ቤት ተሰማ ፡ የዮሴፍ ወንድሞች
መጡ ብለው ነገሩት ፡ ፈርዖንም ደስ አለው ቤተሰቦቹም ።
ፈርዖንም ዮሴፍን አለው ፤ ወንድሞችህን ገንዘባች
ሁን ይዛችሁ ወደ ከነዓን ሂዱ በላቸው ።
አባታችሁን ገንዘባችሁንም ሁሉ ይዛችሁ ወደኔ ኑ የግ
ብጽንም ሀብት ሁሉ እሰጣችኋለሁ የምድርንም ፍሬዋ
ትበላላችሁ ። ዘኁ፡ ፲፰ ፳፭ ፡ ፲፱ ፳፱ ።
አንተም ወንድሞችህን እንዲህ ብለህ እዘዛቸው ፤ ለወ
ንዶች ልጆቻቸው ለሴቶች ልጆቻቸው ለሚስቶቻቸውም
የግብጽ ሠረገሎችን ይውሰዱ አባታቸውንም ያምጡት ።
ለጥቃቅን ዕቃቸው ዓይናቸው ያየችውን ሁሉ አያ
ስቡ የግብጽ በረከት ሁሉ ለነሱ ነውና ።
የእስራኤልም ልጆች እንዳላቸው አደረጉ ፡ ዮሴፍም
የግብጽ ንጉሥ ፈርዖን እንዳለው ሠረገሎችን ሰጣቸው
ለመንገድም ስንቃቸውን ሰጣቸው ። ዘኁ፡ ፫ ፲፯ ።
ሁለት ሁለት ልብሰንም ሰጣቸው ለብንያም ግን ሦስት
መቶ ብርና እያፈራረቀ የሚለብሰው አምስት ልብስ ሰጠ
ው ፡ ላባታቸውም እንዲሁ ። ፪ ነገሥ፡ ፭ ፭ - ፳፫ ።
ከግብጽ የሚገኘውን ሀብት ሁሉ የሚጫኑ አሥር ወደ
ልጋዞች ፡ ለአባቱም በመንገድ ስንቅ የሚጫኑ አሥር በቅ
ሎች ሰደደ ። ፪ ዜና መዋ፡ ፲፩ ፳፫ ። ዳን፡ ፩ ፲፪ - ፳፩ ።
(ዮሴፍም) ወንድሞቹን በጕዳና እርስ በርሳችሁ አት
ጣሉ ብሎ አሰናበታቸው ። መዝ፡ ፩ ፩ ።
ከግብጽም አገር ወጥተው ወደ ከነዓን ሄደው ወደ አባ
ታቸው ዘንድ ደረሱ ።
ልጅህ ዮሴፍ በሕይወት አለ እሱ ለግብጽ አገርና ለአ
ውራጃዋም ሁሉ ገዥ እሱ ነው ብለው ነገሩት (ያዕቆብም)
ልቡ ደነገጠበት አላመናቸውም ።
ዮሴፍ ያላቸውን ነገር የተናገራቸውንም ነገር ሁሉ
ነገሩት ዮሴፍ የላከለትን ሠረገላዎችን በየ ጊዜም ያባታ
ቸው የያዕቆብ ልቡ ተመለሰ ሰውነቱንም ደስ አለው ።
ያዕቆብም ልጄ ዮሴፍ በሕይወት ካለ ይህ ለኔ ትልቅ
ነገር ነው ፤ ሳልሞት እንዳየው እሄዳለሁ አለ ።

ምዕራፍ ፵፮ ።

እስራኤልም ገንዘቡን ሁሉ ይዞ ተነሣ ፡ ወደ ቤርሳቤ
ህም ደርሶ ለአባቱ ለይስሐቅ ፈጣሪ መሥዋዕትን ሠዋ ።

እግዚአብሔርም እስራኤልን በሕልም "ያዕቆብ ያዕ
ቆብ„ ብሎ ጠራው ምንድነው ፤ አለ ።
አለውም የአባቶችህ አምላክ እኔ ነኝ ወደ ግብጽ
አገር መውረድን አትፍራ ፡ በዚያ ትልቅ ሕዝብ አደ
ርግሃለሁና ።
እኔ ወደ ግብጽ አገር አብሬህ እወርዳለሁ ፡ በዚያም

ምስሌከ ዘልፈ ወዮሴፍ ወልድከ ይከድነከ አዕይንቲከ ፡

፭ ወተንሥአ ያዕቆብ እምዐዘቅተ መሐላ ወነሥእዎ ደቂቁ ለያዕቆብ እስራኤል አቡሆሙ ወንዋዮሙኒ ምስሌሆሙ ወአንሶትያሆሙኒ ዲበ ሰረገላት ዘፈነወ ዮሴፍ በዘያመጽእዎሙ ።

፮ ወነሥኡ ንዋዮሙ ወኵሎ ጥሪቶሙ ዘአጥረዩ በምድረ ከነአን ወበአ ያዕቆብ ብሔረ ግብጽ ወኵሉ ዘርኡ ምስሌሁ ፡

፯ ደቂቁ ወደቂቀ ደቂቁ ወአዋልዲሁ ወአዋልደ አዋልዲሁ ምስሌሁ ፡

፰ ወከመዝ ውእቱ አስማቲሆሙ ለደቂቀ እስራኤል እለ በኡ ብሔረ ግብጽ በኵሩ ለያዕቆብ ሮቤል ፡

፱ ወደቂቀ ሮቤል ሄኖኅ ወፍሉስ ወአስሮን ወከርሚ ፡

፲ ወደቂቀ ስምዖን የሙኤል ወያሚን ወአኦድ ወያኩን ወሱሐር ወሰኡል ዘእምነ ከናናዊት ።

፲፩ ወደቂቀ ሌዊ ገርሶን ወቀዓት ወሜራሪ ፡

፲፪ ወደቂቀ ይሁዳ፤ ኤር ወአውናን ወሴሎም ወፋሬስ ወዛራ ወሞቱ ኤር ወአውናን በምድረ ከነአን ወእሉ እሙንቱ ደቂቀ ፋሬስ ኤስሮም ወይሞሔል ፡

፲፫ ወደቂቀ ይሳኮር ቶላዕ ወፎሓ ወያሱብ ወሰምራ ፡

፲፬ ወደቂቀ ዛብሎን ሳሬድ ወአሎን ወአሴል ፡

፲፭ ወእሉ እሙንቱ ደቂቀ ልያ ዘወለደት ለያዕቆብ በመስጴጦምያ ዘሶርያ ወዲና ወለቱ ወኵሉ ነፍስ ደቂቅ ወአዋልድ ሠላሳ ወአርባዕቱ ፡

፲፮ ወደቂቀ ጋድ ስፎን ወሐግ ወሱኒ ወአዜን ወአድ ወአሮሐድ ወአሪሔል ፡

፲፯ ወደቂቀ አሴር ኢያምን ወኢያሱ ወኢዩል ወበርያ ወሣራ እኅቶሙ ወእሉ እሙንቱ ደቂቀ በርያ ከበር ወሜልኪየል ፡

፲፰ ወእሉ እሙንቱ ደቂቀ ዘለፋ እንተ ወሀባ ላባ ለልያ ወይእቲ ዘወለደት ለያዕቆብ ዐሠርቱ ወስድስቱ ነፍስ እሙንቱ ፡

፲፱ ወደቂቀ ራሄል ብእሲተ ያዕቆብ ዮሴፍ ወብንያም ፡

፳ ወተወልዱ ሎቱ ደቂቅ ለዮሴፍ በብሔረ ግብጽ ዘወለደት ሎቱ ወለተ ጴጤፌራ አስኔት ወለተ ማሬ ዘሀገረ ሄልዮቱ ምናሴ ወኤፍሬም ፡

፳፩ ወደቂቀ ምናሴ ዘወለደት ሎቱ ዕቅብቱ ሶርያዊት ማኪር ወማኪር ወለዶ ለገለአድ ወደቂቀ ኤፍሬም እኁሁ ለምናሴ ሱታላ ወጠኀን ወደቂቀ ሱታላ ኤዴን ፡

፳፪ ወደቂቀ ብንያም ቤላ ወቦኮር ወአሲቤር፤ ወእሉ እሙንቱ ደቂቀ በዕል ጌራ ወኖሔማን ወኤሒ ወሮስ ወመፌም ወጌራ ወለዶ ለአራድ ፡

ሁል ጊዜ እኔ ከአንተ ጋር እኖራለሁ፤ ልጅህ ዮሴፍም ዓይኖችህን ያብሳል (ያማውተሃል)። ዘፍ፤ ፲፭ ፲፯ ።

ያዕቆብም ከቤርሳቤህ ተነሣ፤ የያዕቆብም ልጆች አባታቸው ያዕቆብ እስራኤልን ወሰዱት፤ ገንዘባቸውንም ልጆቻቸውንና ሚስቶቻቸውንም አብረው እነሱን እንዲያመጡባቸው ዮሴፍ በላካቸው ሠረገሎች ጫኑ ።

ጓዛቸውንም በከነዓን አገር ያጠራቀሙትን ገንዘባቸውንም ሁሉ ወሰዱ፤ ያዕቆብም ወደ ግብጽ አገር ገባ፤ ዘሩም ሁሉ ከሱ ጋራ ።

ወንዶች ልጆቹ የልጅ ልጆቹ፤ የሴቶች ልጆቹ የሴቶች ልጆቹም ልጆች ከሱ ጋራ ገቡ ። መዝ፤ ፻፭ ፳፫ ።

ወደ ግብጽ አገር የገቡ የያዕቆብ ልጆች ስማቸው እንዲህ ነው፤ የያዕቆብ የበኵር ልጅ ሮቤል ።

የሮቤልም ልጆች ሄኖህ ፍሉስ አሥሮንና ከርሚ ናቸው ። ፩ ዜና መዋ፤ ፩ ፳፱ ።

የስምዖንም ልጆች የሙኤል ያሚን አኦድ ያኩን፤ ሱሐር፤ ከከናናዊቱ የተወለደው ሰኡል ፡

የሌዊም ልጆች ገርሶን ቀዓትና ሜራሪ ።

የይሁዳም ልጆች ኤር፤ አውናን፤ ሴሎም፤ ፋሬስና ዛራ፤ ናቸው ኤርና አውናን ግን በከነዓን አገር ሙተዋል፤ የፋሬስ ልጆችም እሊህ ናቸው፤ ኤስሮምና ይሞሔል ፡

የይሳኮር ልጆች ቶላዕ፤ ፎሐ፤ ያሱብና ስምራ ናቸው ። ፩ ዜና መዋ፤ ፯ ፩ ።

የዛብሎንም ልጆች ሳሬድ፤ አሎንና አሴል ናቸው ።

የሶርያ ክፍል በምትሆን በመስጴጦምያ ልያ ለያዕቆብ የወለደችለት ልጆች እሊህ ናቸው፤ ዲናም ሴት ልጇዋ የልያም ልጆች የሆኑ ሁሉ ሴቱም ወንዱም ሠላሳ አራት ነፍስ ናቸው ። ዘፍ፤ ፳፱ ፴፤ ፴፪ ፳፩ ።

የጋድም ልጆች ስፎን፤ ሐን፤ ሐግ፤ ሱኒ፤ አዜን፤ አድ፤ አሮሔድና አርሔል ናቸው ። ዘኍ፤ ፳፮ ፲፭፤ ፲፮ ፲፯ ።

የያሴር ልጆች ኢያምንና ኢያሱ ኢዩል በርያ እኅታቸው ሣራም የበርያም ልጆች እሊህ ናቸው፤ ከበርና ሚልኪየል ። ፩ ዜና መዋ፤ ፯ ፴ ።

ላባ ለልያ የሰጣት የዘለፋም ልጆች እሊህ ናቸው፤ እሷም ለያዕቆብ የወለደችለት ልጆች አሥራ ስድስት ነፍስ ናቸው ።

የያዕቆብ ሚስት የራኄል ልጆችም ዮሴፍና ብንያም ናቸው ።

ለዮሴፍም በግብጽ አገር ልጆች ተወለዱለት እሊህም የሄልዮቱ አገር ካህን የሚሆን የጴሜጤፌራ ልጅ አስኔት የወለደችለት ናቸው ።

የሶርያ ወገን የሆነች አገልጋዩ ለምናሴ የወለደችለት ማኪር፤ ማኪርም ገለአድን ወለደ፤ የምናሴ ወንድም የኤፍሬም ልጆች ሱታላ ጠኀን፤ የሱታላም ልጅ ኤዴን ነው ።

የብንያም ልጆች ቤላ፤ ቦከር፤ አሲቤር፤ የቤላም ልጆች ጌራ፤ኖሔማን፤ኤሒ፤ሮስ፤ መፌም ናቸው፤ ጌራም አራድን ወለደ

፳፪ ወእሉ እሙንቱ ደቂቀ ራሔል ዘወለደት ለያዕቆብ ዐሥርቱ ወአርባዕቱ ነፍስ ።
፳፫ ወደቂቀ ዳን አሳ ።
፳፬ ወደቂቀ ንፍታሌም አሴሔል ወጎሂን ወየሴር ወሴሌም ።

፳፭ እሉ እሙንቱ ደቂቀ በላ እንተ ወሀበ ላባ ለራኄል ወለቱ ወወለደቶሙ ለእሉ ለያዕቆብ ወኵሉ ነፍስ ዘወለደት ባላ ሰብዓቱ ።
፳፮ ወኵሉ ነፍስ ዘበአ ብሔረ ግብጽ ምስለ ያዕቆብ ዘእንበለ አንስትያ ደቂቁ ስሳ ወሰብዓቱ ።
፳፯ ወደቂቀ ዮሴፍ እለ ተወልዱ ሎቱ በብሔረ ግብጽ ክልኤቱ ፡ ወኮነ ኵሉ ነፍስ እንተ በአት ብሔረ ግብጽ ምስለ ያዕቆብ ሰብዓ ።
፳፰ ወለይሁዳ ፈነዎ ቅድሜሁ ኀበ ዮሴፍ ከመ ይትቀበሎ ውስተ ምድረ ራምሴ እንተ ስማ ቃቴሮአስ ።
፳፱ ወእንሥአ ዮሴፍ ሠረገላቲሁ ወሖረ ይትቀበሎ ለያዕቆብ አቡሁ ውስተ ምድረ ቃቴሮአስ ፡ ወሶበ ረከቦ ሐቀፎ ክሳዶ ወበከየ ዐቢየ ብካየ ።
፴ ወይቤሎ እስራኤል ለዮሴፍ እምይእዜሰ ለእሙት እን ከ እስመ ርኢኩ ገጸከ እንዘ ሕያው አንተ ።
፴፩ ወይቤሎሙ ዮሴፍ ለአኃዊሁ አሐውር እንግሮ ለፈርዖን ወእብሎ አኃውየ ወቤተ አቡየ እለ ሀለዉ በምድረ ከነአን መጽኡ ኀቤየ ።
፴፪ ወኖሎተ እንስሳ ወሰብአ መራዕይ እሙንቱ ሰብእ ወአባግዒሆሙ ወአልሕምቲሆሙ ወኵሎ ንዋዮሙ አምጽኡ።

፴፫ ወእመ ጸውዐክሙ ፈርዖን ወይቤለክሙ ምንት ተግባርክሙ በልዎ ኖሎተ እንስሳ ንሕነ አግብርቲከ እምንእስነ እስከ ይእዜ ወአበዊነሂ ከማሁ ከመ፡ከመ ትኅድሩ ምድረ ጌሴም እንተ ዓረብ ።
፴፬ እስመ ያስቆርርዎሙ ሰብአ ግብጽ ለኵሎሙ ኖሎተ አባግዕ ።

ምዕራፍ ፵፯ ።

፩ ወበአ ዮሴፍ ወነገሮ ለፈርዖን ወይቤሎ አቡየ ወአኃውየ ምስለ እንስሳሆሙ ወንዋዮሙ መጽኡ እምድረ ከነአን ወናሁ በጽሑ ውስተ ምድረ ጌሴም ።
፪ ወነሥአ ዮሴፍ ኃምስተ እደወ እምአኃዊሁ ወአብጽሖሙ ምስሌሁ ኀበ ፈርዖን ።
፫ ወይቤሎሙ ፈርዖን ለአኃዊሁ ለዮሴፍ ምንት ተግባርክሙ ወይቤልዎ ኖሎተ እንስሳ ንሕነ አግብርቲከ ወአበዊነሂ ።
፬ ወይቤልዎ ለፈርዖን አኅድረነ ውስተ ምድር እንተ ኀበ መጻእነ እስመ አልቦ ምርዐይ ለእንስሳ አግብርቲከ ወጸንዐ ረኃብ ውስተ ምድረ ከነአን ፡ ወይእዜኒ አኅድረነ ለአግብርቲከ ውስተ ምድረ ጌሴም ።
፭ ወይቤሎ ፈርዖን ለዮሴፍ እምከመ መጽኡ አቡከ ወአኃዊከ ኀቤከ ናሁ ኵላ ምድረ ግብጽ ቅድሜከ ይእቲ ውስተ እንተ ትኄይስ ምድር ይኅድሩ ።

ለያዕቆብ የወለደችለት የራኄል ልጆች እሊህ ናቸው አሥራ አራት ነፍስ ናቸው ።
የዳን ልጅ አሳ ነው ። ዘኍ፡ ፳፮ ፵፪ ።
የንፍታሌም ልጆች አሴሔል ፡ ጎሂን ፡ ዮሴር ሴሌም ፡ ናቸው ። ፩ ዜና መዋ፡ ፯ ፲፫ ።
ባላ ለልጅዋ ለራኄል የሰጣት የባላ ልጆችም እሊህ ናቸው ፤ ለያዕቆብ እኒህን የወለደችለት ባላ የወለደቻቸው ነፍስ ሁሉ ሰባት ናቸው ። ዘፍ፡ ፴ ፫-፰ ።
ከልጆቹ ሚስቶች በቀር ከያዕቆብ ጋራ ወደ ግብጽ አገር የገቡት ስሳ ሰባት ሰዎች ናቸው ። ዘፀ፡ ፩ ፭ ።
በግብጽ ለዮሴፍ የተወለዱለት ልጆች ሁለት ናቸው ፤ ከያዕቆብም ጋራ ግብጽ የገባው ሰው ሰባ ሆነ ።
ዘዳ፡ ፲ ፳፪ ፡ ግብ፡ ሐዋ፡ ፯ ፲፬ ።
ስሟ ቃቴሮአስ እስከ ምትባል እስከ ራምሴ ድረስ ይቀበለው ዘንድ ይሁዳን አስቀድሞ ወደ ዮሴፍ ላከው ።
ዮሴፍም አባቱ ያዕቆብን ይቀበለው ዘንድ ሠረገላውን ጭኖ ወደ ቃቴሮአስ ሄደ ፡ ባገኘውም ጊዜ አንገቱን አቅፎ እጅግ አለቀሰ ።
እስራኤልም ዮሴፍን አንተ በሕይወት ሳለህ ፊትህን አይቻለሁና እንግዲህስ ልሙት አለው ።
ዮሴፍም ወንድሞቹን እንዲህ አላቸው ፤ ለፈርዖን እንዲህ ብዬ እነግረዋለሁ በከነዓን ምድር የሚኖሩት ወንድሞቼ የአባቴ ወገኖች ወደ እኔ መጡ ። ዘፍ፡ ፵፯ ፩ ።
ከብት የሚጠብቁ መንጋ የሚያረቡ ናቸው ፡ ከብቶችን ለማሳደግ ዕውቀት ያላቸው ሰዎች ናቸው ፤ በጎቻቸውን ላሞቻቸውን ገንዘባቸውን ሁሉ አምጥተዋል ።
ፈርዖን ጠርቶ ሥራችሁ ምንድነው ቢላችሁ ፤ እኛ አገልጋዮችህ ከሕፃንነታችን ጀምሮ እስከዛሬ ከብት አርቢዎች ነን ፡ አባቶቻችንም ፈጽመው እንደዚሁ ነበሩ በሉት ፡ በምዕራብ በኩል ባለችው በጌሴም እንድትቀመጡ።
የግብጽ ሰዎች በግ አርቢዎችን ሁሉ ይጸየፍዋቸዋልና ።

ምዕራፍ ፵፯ ።

ዮሴፍ ገብቶ ወንድሞቼና አባቴ ከጓዛቸውና ከከብቶቻቸው ጋራ ከከነዓን አገር መጡ ፡ እነሆም ወደ ምድረ ጌሴም ደረሱ ብሎ ለፈርዖን ነገረው ። ዘፍ፡ ፵፮ ፴፩ ።
ዮሴፍም ከወንድሞቹ አምስት ሰዎችን አምጥቶ ከሱ ጋራ ወደ ፈርዖን አደረሳቸው ። ግብ፡ ሐዋ፡ ፯ ፲፫ ።
ፈርዖንም የዮሴፍን ወንድሞች ሥራችሁ ምንድነው ፤ አላቸው ፡ እነሱም እኛ አገልጋዮችህ ከብት አርቢዎች ነን አባቶቻችንም (ዘላኖች) ናቸው አሉት ።
ፈርዖንንም በመጣንበት አገር አሳድረን ለባሮችህ ከብቶች መሠማሪያ የለምና በከነዓን ምድርም ረኃብ ፀንቶ አልና አሁንም (እኛን) ባሮችህን በጌሴም ምድር አኑረን አሉት ። ዘዳ፡ ፳፮ ፭ ።
ፈርዖንም ዮሴፍን እነሆ አባትህና ወንድሞችህ ወዳንተ ከመጡ የግብጽ አገር ሁሉ በፊትህ ናት በምትሻለው ምድር ይኑሩ ።

፮ ወእመኒ ተአምር ከመ በሙ ጽኑዓን እደው በውስቴቶሙ ሢሞሙ መላእክተ ኖሎት ለእንስሳየ ።

ከእነሱም መካከል ብርቱዎች እንዳሉ ብታውቅ ለከብቶቼ የዘላኖች አለቆች አድርገህ ሹማቸው አለው ።

፯ ወአብአ ዮሴፍ ለአቡሁ ወአቀሞ ቅድመ ፈርዖን ወተአምኖ ያዕቆብ ለፈርዖን ።

ዮሴፍም አባቱን አግብቶ በፈርዖን ፊት አቆመው፤ ያዕቆብም ፈርዖንን እጅ ነሣው ።

፰ ወይቤሎ ፈርዖን ለያዕቆብ ሚ መጠን መዋዕል ዘሐየውከ ።

ፈርዖንም ያዕቆብን (በዚህ ዓለም) የኖርከው ዘመን ምን ያህል ነው፤ አለው ። ፪ ሳሙ፤ ፲፱ ፴፬ ።

፱ ወይቤሎ ያዕቆብ ለፈርዖን መዋዕለ ሕይወትየሰ ዘሐየውኩ ምእት ወሠላሳ ዓመት እማንቱ ኅዳጣት ዓመታት ወእኩያተ ኮናኒ መዋዕለ ሕይወትየሰ ወንመታትየኒ ከመ ወኢምንት ኮናኒ በኀበ መዋዕለ ሕይወተ አበውየ ዘሐይዉ ።

ያዕቆብም ፈርዖንን በሕይወት የኖርኩበት ዘመኔስ መቶ ሠላሳ ዓመታት ናቸው ጥቂት ዓመታት ናቸው እንዚህም ክፉዎች ሆኑብኝ በሕይወት የኖርኩባቸው ዘመኖች ዓመቶችም አባቶቼ በኖሩባቸው የሕይወት ዘመናት መጠን እንደ ኢምንት ናቸው አለው ። መዝ፤ ፴፱ ፲፪ ።

፲ ወበረከ ያዕቆብ ለፈርዖን ወወፅአ እምኀቤሁ ።

ያዕቆብም ፈርዖንን መርቆት ከሱ ዘንድ ወጣ ።

፲፩ ወአኅደሮሙ ዮሴፍ ለአቡሁ ወለአኀዊሁ ወወሀቦሙ ምክናነ በምድረ ግብጽ ውስተ እንተ ትኄይስ ምድር ውስተ ምድረ ራምሴ ዘአዘዘ ሎሙ ፈርዖን ።

ዮሴፍም ወንድሞቹንና አባቱን በምድረ ግብጽ ግዛት ሰጥቶ ፈርዖን በዘዘላቸው በመልካሚቱ ምድር በራምሴ አኖራቸው ። ዘፀ፤ ፳ ፲፩፤ ፲፪ ፴፯ ።

፲፪ ወዮሴፍ ይሰፍር ሥርናየ ሲሳየ ለአቡሁ ወለአኀዊሁ ወለኵሉ ቤተ አቡሁ ለለአሐዱ ነፍስ ይሰፍር ሥርናየ ።

ዮሴፍም ለአባቱና ለወንድሞቹ ላባቱም ቤተሰቦች ሁሉ ምግብ የሚሆን ሥንዴን ይሰፍር ነበር፤ ለእያንዳንዱም ነፍስ ምግብ ሥንዴን ይሰፍር ነበር ።

፲፫ ወአልቦ ሥርናይ ውስተ ኵሉ ምድረ ግብጽ እስመ ፀንዐ ረኃብ ጥቀ፤ ወኀልቀ በረኃብ ብሔረ ግብጽ ወከነአን ።

በመላ የግብጽ አገር ሥንዴ አልነበረም፤ ረኃብ እጅግ ጸንቷልና የግብጽና የከነዓን አገር በረኃብ አለቀ ።

፲፬ ወአስተጋብአ ዮሴፍ ኵሎ ወርቀ ዘአምጽኡ ሰብአ ግብጽ ወሰብአ ከነአን ሤጠ እክል ዘሤጠ ሎሙ ወአብአ ዮሴፍ ኵሎ ወርቀ ውስተ ቤተ ፈርዖን ።

ዮሴፍም የሸመተላቸውን የእኽሉን ዋጋ የሆነ የግብጽና የከነዓን ሰዎች ያመጡለት የእኽል ዋጋ የሆነውን ወርቅ ሁሉ ሰብስቦ ወርቁንም በሙሉ ወደ ፈርዖን ቤት አገባ ። ዘፍ፤ ፵፩ ፶፩ ።

፲፭ ወኀልቀ ኵሉ ወርቅ ዘብሔረ ግብጽ ወዘኵሉ ብሔረ ከነአን፤ ወመጽኡ ወበኡ ኵሉ ሰብአ ግብጽ ኀበ ዮሴፍ ወይቤልዎ ሀበነ እክለ ከመ ኢንሙት በቅድሜከ እስመ ኀልቀ ወርቅነ ።

በግብጽ አገር በከነዓን አገር ያለ ወርቅ ሁሉ አለቀ፤ የግብጽም ሰዎች ሁሉ ወደ ዮሴፍ መጥተው ወርቃችን አልቆአልና በፊትህ እንዳንሞት እኽል ስጠን አሉት ።

፲፮ ወይቤሎሙ ዮሴፍ አምጽኡ እንስሳክሙ ወእሁበክሙ እክለ ህየንተ እንስሳክሙ እመ ኀልቀ ወርቅክሙ ።

ዮሴፍም ወርቃችሁ ካለቀ ከብቶቻችሁን አምጡና ስለ ከብቶቻችሁ ፈንታ እኽልን እሰጣችኋለሁ አላቸው ።

፲፯ ወአምጽኡ እንስሳሆሙ ኀበ ዮሴፍ ወወሀቦሙ እክለ ህየንተ አብግዒሆሙ ወአልሕምቲሆሙ ወህየንተ አእዱጊሆሙ ወሴሰዮሙ እክለ በይእቲ ዓመት ።

ከብቶቻቸውንም ወደ ዮሴፍ አመጡ፤ እሱም ስለላሞቻቸውና ስለበጎቻቸው ስለአህዮቻቸውም ፈንታ እኽልን ሰጣቸው፤ በዚያችም ዓመት እኽልን መገባቸው ።

፲፰ ወተፈጸመት ይእቲ ዓመት ወመጽኡ ኀቤሁ በካልእት ዓመት ወይቤልዎ ሀበነ እክለ ከመ ኢንሙት ወኢንኅልቅ ለእግዚእነ እስመ ተወድአ ወርቅነሂ ወንዋይነሂ ወእንስሳነሂ ወአኅለቅናሁ ለኵሉ እግዚኦ ወአልቦ ዘተርፈ ለነ በቅድሜከ እግዚኦ ዘእንበለ ሥጋ ዚአነ ወምድርነ ።

ያችም ዓመት አለቀች በሁለተኛውም ዓመት ወደሱ መጥተው እንዲህ አሉት፤ እንዳንሞት እኽል ስጠን ለጌታችንም ረኃብ እንዳናልቅበት ወርቃችንም ከብታችንም አልቋል ገንዘባችንም ሁሉ ተጨርሷልና አቤቱ፤ ሁሉን ሽጠን ጨረስነው፤ ከሰውነታችንና ከምድራችን በቀር በፊትህ ለእኛ የቀረን ነገር የለም አሉት ።

፲፱ ከመ ኢንሙት እንከ በቅድሜከ ወምድርነኒ ከመ ኢትማስን ንሥአነ ወአጥርየነ ኪያነሂ ወምድረነሂ ህየንተ እክል ወንኩን አግብርተ ለፈርዖን ህየንተ እክል ወምድርነሂ ትኩን ሎቱ ወሀበነ ዘርአ ከመ ንዝራእ ከመ ንሕየው ወኢንሙት ወምድርነሂ ከመ ኢትማስን ።

እንግዲህ በፊትህ እንዳንሞት ምድራችንም እንዳትጠፋ ስለ እኽል ፈንታ እኛንም ምድራችንንም ይዘን ግዛን፤ እኛም ለፈርዖን ባሮች እንሁን፤ ምድራችንም ለሱ ትሁን፤ እንዳንሞት እንድን ዘንድ ምድራችንም እንዳትጠፋ እንድንዘራ ዘርን ስጠን ።

፳ ወአጥረየ ዮሴፍ ኵሎ ምድሮሙ ለግብጽ ወአግብአ ለፈርዖን ኵሎ ምድሮሙ እስመ ኀየሎሙ ረኃብ ወኮነ ኵሉ ምድር ለፈርዖን ።

ረኃብም በርትቶባቸዋልና ዮሴፍ የግብጽ ምድራቸውን ሁሉ ገዝቶ ለፈርዖን አገባው፤ ምድሩም ሁሉ ለፈርዖን ሆነ ።

፳፩ ወኵሉ ሕዝብ ኮንዎ አግብርቲሁ ወቀነዮሙ እምአጽናፈ ምድር ወእድባሪሆሙኒ ወኵሎ ደወሎሙ ለግብጽ

ሕዝቡም ሁሉ ባሮቹ ሆኑ ከዳር እስከዳርም ገዛቸው ጕልታቸውንም አገራቸውንም ሁሉ እስከ ከነዓን ምድር

እምአጽናፈ ደወሎሙ ለከነአን ዘእንበለ ምድሮሙ ለማርያን በሕቲቶ ዘኢያጥረየ ዮሴፍ።
፳፪ እስመ ወሀበሙ ፈርዖን ለማርያን ወፈተቶሙ ወጸገዎሙ ወበእንተ ዝ ኢሤጡ ምድሮሙ።
፳፫ ወይቤሎሙ ዮሴፍ ለኵሎሙ ሰብአ ግብጽ ናሁ ተሣየጥኩክሙ ኪያክሙኒ ወምድረክሙኒ ለፈርዖን፡ ንሥኡ ለክሙ ዘርአ ወዝርእዋ ለምድርክሙ።
፳፬ ወታገብኡ ለፈርዖን እክለ ኃምስተ እደ ወአርባዕቱ እድ ለክሙ ዘይከውንክሙ ዘርአ ለምድርክሙ ወለሲሳይክሙ ወለሲሳየ ኵሉ ሰብእክሙ።
፳፭ ወይቤልዎ አሕየውከነ ወረከብነ ሞገሰ በቅድሜሁ ለእግዚእነ ወከነ አግብርተ ለፈርዖን።
፳፮ ወከነት ዛቲ ሥርዓት እንተ ሠርዐ ዮሴፍ ውስተ ምድረ ግብጽ ወቆመት እስከ ዛቲ ዕለት ከመ ያግብኡ ኃምስተ እደ ለፈርዖን እስከ ዮም ዘእንበለ ምድረ ማርያን በሕቲታ እንተ ኢከነት ለፈርዖን።
፳፯ ወነበረ እስራኤል ውስተ ጌሴም ወከነት ይእቲ ክፍሎሙ ወበዝኁ ወመልኡ ጥቀ።
፳፰ ወሐይወ ያዕቆብ በምድረ ግብጽ ዐሠርተ ወሰብዓተ ዓመተ፡ ወከነ ኵሉ ዓመተ ሕይወቱ ለያዕቆብ ምእተ ወአርብዐ ወሰብዓተ ዓመተ።
፳፱ ወቀርበ መዋዕሊሁ ለእስራኤል ለመዊት ወጸውዖ ለዮሴፍ ወልዱ ወይቤሎ እመ ረከብኩ ሞገሰ በቅድሜከ ደይ እዴከ ላዕለ እዴየ ወግበር ምስሌየ ምሕረተ ወጽድቀ ከመ ኢትቅብረኒ ውስተ ምድረ ግብጽ ዳእሙ ከመ እኑም ምስለ አበውየ።
፴ ወአውጽአኒ እምብሔረ ግብጽ ወቅብረኒ ውስተ መቃብሮሙ ለአበውየ፡ ወይቤሎ ዮሴፍ አሆ እገብር ለከ ዘትቤለኒ።
፴፩ ወይቤሎ መሐልኬ ሊተ፡ ወመሐለሎቱ ወሰገደ እስራኤል ውስተ ከተማ በትሩ (ላዕለ ርእሰ ዓራቱ)።

ምዕራፍ ፵፰።

፩ ወከነ እምድኅረ ዝንቱ ነገር ይቤልዎ አኃዊሁ ለዮሴፍ ደክመ አቡነ፡ ወነሥአ ዮሴፍ ክልኤተ ደቂቆ ምናሴሃ ወኤፍሬምሃ።
፪ ወይቤልዎ ለእስራኤል ናሁ ወልድከ ዮሴፍ መጽአ ኀቤከ ወተኀየለ እስራኤል ወተንሥአ ነበረ ዲበ ምስከቢሁ።
፫ ወይቤሎ ያዕቆብ ለዮሴፍ አምላኪየ ዘአስተርአየኒ በሎዛ በምድረ ከነአን ባረከኒ።
፬ ወይቤለኒ ናሁ አነ አበዝኀከ ወአስተበዝኀከ ወእገብረከ ማኅበረ አሕዛብ ወእሁበከሃ ለዛቲ ምድር ወለዘርእከኒ እምድኅሬከ ከመ ይምልክዋ ለዓለም።
፭ ወይእዜኒ እሉ ደቂቅከ ክልኤቱ ኤፍሬም ወምናሴ እለ ተወልዱ ለከ በብሔረ ግብጽ ዘእንበለ እምጻእ አነ ዝየ ኀቤከ ከመ ሮቤል ወስምዖን ሊተ እሙንቱ።
፮ ወአመበ ዘወለድከ እምይእዜ በአስማተ አበዊሆሙ

ድንበር ድረስ፡ ዮሴፍ ከልገዛው ከካህናት ጣአቱ በቀር ሁሉንም ሁዳድ አደረገው።
ፈርዖን ለካህናት ድርጎ ሰጥቷቸዋልና ፈርዖን የሰጣቸውንም ይመገቡሉና ስለዚህ ምድራቸውን አልሸጡም።
ዮሴፍም የግብጽን ሰዎች ሁሉ እንዲህ አላቸው እናንተንም ምድራችሁንም እነሆ ለፈርዖን ገዝቻችኋለሁ ዘር ወስዳችሁ ምድራችሁን ዝሩአት።
አምስቱን እጅ ለፈርዖን ታገባላችሁ፡ አራቱ እጅ ለምድራችሁ ዘር ለናንተና ለቤተ ሰቦቻችሁም ሁሉ ምግብ ይሆናችኋል።
(በረኃብ ከመሞት) አንተ አዳንከን በጌታችንም ፊት ሞገስ አገኘን፡ ለፈርዖንም ባሮች ሆነን አሉት።
ለፈርዖን ከልሆነች ከካህናቱ ምድር ብቻ በቀር እስከ ዛሬ ድረስ ለፈርዖን አምስት እጅ ያገቡ ዘንድ ዮሴፍ የሠራት ይህች ሕግ እስከዚች ቀን ድረስ በግብጽ አገር ሥርዓት ሆና ጸናች። ዘፍ፡ ፵፯ ፳፪።
እስራኤልም በጌሴም አገር ኖረ፡ እሷም ክፍላቸው ሆነች፡ መሉ እጅግም በዙ። ዘፍ፡ ፵፰ ፲።
ያዕቆብም በምድረ ግብጽ አሥራ ሰባት ዓመት ኖረ፡ የያዕቆብ መላው የሕይወቱ ዘመን ፻፵፯ ዓመት ሆነ።

ያዕቆብም የሚሞትበት ቀን በደረሰ ጊዜ ልጁ ዮሴፍን ጠርቶ እንዲህ አለው፤ በፊትህ ሞገስ አግኝቼ እንደሆነ በጅህ እጄን ምታ በግብጽ ምድር እንዳትቀብረኝ ምሕረትንና ቸርነትን አድርግልኝ፡ ከአባቶቼ ጋር ላንቀላፋ እንጂ። ዘዳ፡ ፴፩ ፲፬፡ ፩ ነገ፡ ፪ ፩።
ከግብጽ ምድር አውጥተህ በአባቶቼ መቃብር ቅበረኝ ዮሴፍም እሺ ያልከኝን አደርግልሃለሁ አለው።
ማልልኝም አለው (እሱም) ማለለት ያዕቆብም ወደ አልጋው ራስጌ ዘንበል አለ። ፩ ነገ፡ ፴፫ ፪። ዕብ ፲፩ ፳፩።

ምዕራፍ ፵፰።

ከዚህም ነገር በኋላ እንዲህ ሆነ ወንድሞቹ አባታችን ደከመ ብለው ለዮሴፍ ነገሩት፡ ዮሴፍም ሁለቱን ልጆቹን ኤፍሬምንና ምናሴን ይዞ ሄደ።
ለእስራኤልም እነሆ ልጅህ ዮሴፍ ወደ አንተ መጥቷል ብለው ነገሩት፡ ያዕቆብም ተበረታቶ ተነሥቶ በአልጋው ላይ ተቀመጠ።
ያዕቆብ ዮሴፍን እንዲህ አለው፤ በከነዓን ምድር በሎዛ የተገለጠልኝ ፈጣሪዬ ባረከኝ። ዘፍ፡ ፲፯ ፩።
እኔ አበዛሃለሁ የብዙ ብዙም አደርግሃለሁ የአሕዛብም ጉባኤ አደርግሃለሁ፡ ይህችንም ምድር ለአንተ እሰጥሃለሁ ከንተም በኋላ የዘላለም ርስት ያደርጓት ዘንድ ለዘርህም ብሎኛል። ዘፍ፡ ፲፯ ፲፫።
አሁንም እኔ ወደዚህ ወደ አንተ ሳልመጣ በግብጽ አገር የተወለዱልህ እሊህ ሁለቱ ልጆችህ ኤፍሬምና ምናሴ እንደ ስምዖንና እንደ ሮቤል የኔ ናቸው።
እንግዲህም ወዲህ የምትወልዳቸው ልጆች ቢኖሩ

ይሰመዩ ወይኩኑ ውስተ ክፍለ አኀዊሆሙ ።

፯ ወአመ መጻእኩ እነ እመስጴጦምያ ዘሶርያ ሞተት ራ
ኄል እምከ በምድረ ከነአን በፍኖት ሶበ ቀረብኩ ኀበ ምር
ዋጸ አፍራስ ዘኤፌፍራታ ለበጺሐ ኤፍራታ ወቀበርክዋ
ውስተ ፍኖት ዘምርዋጸ አፍራስ ዘስሙ ቤተ ልሔም ።
፰ ወሶበ ርእየ እስራኤል ደቂቆ ለዮሴፍ ይቤሎ ምን
ትከ እሉ ።
፱ ወይቤሎ ዮሴፍ ለአቡሁ ደቂቅየ ዘወሀበኒ እግዚአብ
ሔር በዝየ፣ ወይቤሎ ያዕቆብ አምጽኦሙ ኀቤየ ከመ
እባርኮሙ ።
፲ ወአዕይንቲሁሰ ለእስራኤል ከብዳ ወተከድና እምርስእ
ወኢይክል ከሢቶተ ወነጽሮ፣ ወአቅረቦሙ ኀቤሁ ወሐቀ
ቀፎሙ ወሰዓሞሙ ።
፲፩ ወይቤሎ እስራኤል ለዮሴፍ ናሁ ኢተፈለጥኩ እምገ
ጽከ ወናሁ ዘርአከኒ አርአየኒ እግዚአብሔር ።
፲፪ ወአውፅኦሙ ዮሴፍ እማእከለ ብረኪሁ ወሰገደ ሎቱ
በገጹ ውስተ ምድር ።
፲፫ ወነሥኦሙ ዮሴፍ ለክልኤቱ ደቂቁ፣ ወአቀሞ ለኤፍ
ሬም በየማኑ ኀበ ፀጋመ እስራኤል፡ ወለምናሴ አቀሞ በፀ
ጋሙ ኀበ የማነ እስራኤል ወአቅረቦሙ ኀበ አቡሁ ።
፲፬ ወሰፍሐ እስራኤል እዴሁ እንተ የማን ወአንበረ ላዕለ
ርእሰ ኤፍሬም ወውእቱ ይንእስ እምእኁሁ፣ ወእዴሁ
እንተ ፀጋም አንበረ ላዕለ ርእሰ ምናሴ ወአስተኀለፈ እደ
ዊሁ ወባረኮሙ ።
፲፭ ወይቤ ውእቱ እግዚአብሔር ዘአሥመርዎ አበውየ
ቅድሜሁ አብርሃም ወይስሐቅ ወእግዚአብሔር ውእቱ
ዘሐፀነኒ ወሴሰየኒ እ ን እስየ እስከ ዛቲ ዕለት ።

፲፮ ወመልአክ እግዚአብሔር ዘአድኀነኒ እምኵሉ እኩይ
ውእቱ ለይባርኮሙ ለእሉ ሕፃናት ወይሰመይ ስምየ በሙ
ወስመ አበውየ አብርሃም ወይስሐቅ ይብዝኁ ወይትበ
ዝኁ ወይምልኡ ዲበ ምድር ።

፲፯ ወሶበ ርእየ ዮሴፍ ከመ አንበረ አቡሁ እዴሁ እንተ
የማን ላዕለ ርእሰ ኤፍሬም ወእዴሁ እንተ ፀጋም ላዕለ
ርእሰ ምናሴ ከነ ሎቱ ክቡደ፣ ወአኀዘ ዮሴፍ እደ አቡሁ
ያስተኃልፍ እምርእሰ ኤፍሬም ላዕለ ርእሰ ምናሴ ።
፲፰ ወይቤሎ ዮሴፍ ለአቡሁ አኮ ከመዝ አባ እስመ ዝንቱ
በኵርየ አንብር እዴከ እንተ የማን ላዕሌሁ ።
፲፱ ወይቤሎ እስራኤል አአምር ወልድየ አአምር፣ ዝኒ
ይከውን ሕዝበ ዓቢየ፣ አላ እኁሁ ዘይንእስ የዐብዮ ወዘ
ርኡ ብዙኀ አሕዛበ ይከውን ።
፳ ወባረኮሙ በይእቲ ዕለት ወይቤ ይትባረክ ብክሙ
አምላከ እስራኤል ወይበሉ ይባርክ እግዚአብሔር ከመ
ኤፍሬም ወምናሴ፣ ወአቅደመ ኤፍሬም እምናሴ ።

፳፩ ወይቤሎ እስራኤል ለዮሴፍ ናሁ አነ እመውት፣ ወየ
ሀሉ እግዚአብሔር ምስሌክሙ ወያግብእክሙ ውስተ ም

ግን በወንድሞቻቸው ስም ይጠሩ፣ በወንድሞቻቸውም
ዕጣ ይግቡ ።
እኔ ከሶርያ ወንዞች መካከል በመጣሁ ጊዜ ኤፍራታ
ለመድረስ ስቃረብ ፈረስ በሚፈትኑበት በከነዓን ምድር
እናትህ ራኄል ሞተች በጐዳና ላይ ወደ ፈረስ መፈተ
ኛው ስሙ ቤተልሔም በሚባለውም መንገድ ቀበርኋት ።
እስራኤልም የዮሴፍን ልጆች ባየ ጊዜ እነዚህ ምኖ
ችህ ናቸው፣ አለው ።
ዮሴፍም አባቱን እግዚአብሔር በዚህ የሰጠኝ ልጆቼ
ናቸው አለው፣ ያዕቆብም ልባርካቸው ወደኔ አምጣቸው
አለው ። ዕብ፣ ፲፩ ፳፩ ።
የእስራኤልም ዐይኖቹ ከእርጅና የተነሣ ፈዘው (ተጨ
ፍነው) ነበር ዓይኑን መግለጥም ማየትም አይችልም ነበር፣
ወደሱም አቀረባቸው አቀፋቸው ሳማቸውም ።
እስራኤልም ዮሴፍን እነሆ ከፊትህ አልተለየሁም እነ
ሆም ዘርህን እግዚአብሔር አሳየኝ አለው ።
ዮሴፍም ከጕልበቱ መካከል ፈቀቅ አደረጋቸው በም
ድር ላይም በግንባሩ ወድቆ ሰገደለት ።
ዮሴፍም ሁለት ልጆቹን አምጥቶ ኤፍሬምን በያዕቆብ
ግራ በሱ ቀኝ አቆመው፣ ምናሴንም በሱ ግራ በያዕቆብ
ቀኝ አቁሞ ወደ አባቱ አቀረባቸው ።
እስራኤልም ቀኝ እጁን ዘርግቶ በኤፍሬም ራስ ላይ
አኖረ እሱም ከወንድሙ ያንስ ነበር፣ ግራ እጁንም በም
ናሴ ራስ ላይ አኖረ፣ እጆቹን አመሳቅሎም ባረካቸው ።
ዘፍ፣ ፵፰ ፲፱ ።
እንዲህም አለ አባቶቼ አብርሃም ይስሐቅ በፊቱ ያገ
ለገሉት እሱ እግዚአብሔር ከሕፃንነቴ ጀምሮ የተከባ
ከበኝ እስከ ዛሬ እስከዚች ቀን ድረስ የመገበኝ እሱ
እግዚአብሔር ነው ። ዘፍ፣ ፲፯ ፩፣ ፳፬ ፵ ።
ከክፉ ነገር ሁሉ ያዳነኝ የእግዚአብሔር መልአክም
እነዚህን ልጆች እሱ ይባርካቸው (ያክብራቸው) ስሜም
በነሱ ይጠራ፣ የአባቶቼ የአብርሃምና የይስሐቅ ስምም
በነሱ ይጠራ ይብዙ፣ የብዙ ብዙም ይሁኑ፣ ምድርንም
ይምሏት ። ፪ ሳሙ፣ ፬ ፱ ። ኢሳ፣ ፵፬ ፳፪ - ፳፫ ።
ዮሴፍም አባቱ ቀኝ እጁን በኤፍሬም ራስ ላይ ግራ
እጁን በምናሴ ራስ ላይ እንዳኖረ በየ ጊዜ ከባድ ነገር
ሆኖበት፣ የአባቱንም እጅ ያዘ ከኤፍሬም ራስ ላይ ወደ
ምናሴ ራስ ላይ ያስተላልፍ ጀመር ። ዘፍ፣ ፳፰ ፰፣ ዘዳ፣ ፳፰ ፲ ።
ዮሴፍም አባቱን አባቴ እንዲህ አይደለም፣ የበኵር
ልጁ ይህ ነውና ቀኝ እጅህን በሱ ላይ አኑር አለው ።
አባቱም አውቃለሁ ልጄ አውቃለሁ ይህም ታላቅ ሕ
ዝብ ይሆናል፣ ይህም ታላቅ ነው ግን ታናሽ ወንድሙ
ይበልጠዋል ዘሩም ብዙ ሕዝብ ይሆናል አለው ።
በዚያችም ቀን ባረካቸው በእና ምክንያት የእስራ
ኤል ፈጣሪ ይክበር (ሰዎች) እንደ ኤፍሬምና እንደ ምናሴ
እግዚአብሔር ይባርክህ ይበሉ አለ፣ ኤፍሬምን ከምናሴ
አስቀደመ ። ሩት ፬ ፲፩ ፲፪ ።
እስራኤልም ዮሴፍን እንዲህ አለው፣ እነሆ እኔ እሞ
ታለሁ እግዚአብሔር ከናንተ ጋር ይኑር ወደ አባቶቻችሁ

ድረ አበዊክሙ ።
፳፪ ወአነ እሁበከ ምህርከ ሠናየ ዘይኄይስ እም፲ አኀዊከ ዘነሣእኩ እምእዴሆሙ ለአሞሬዎን በቀስትየ ወበኲናትየ።

ምዕራፍ ፵፱ ።

፩ ወጸውዖሙ ያዕቆብ ለደቂቁ ወይቤሎሙ ተጋብኡ ኀቤየ ወእየድዓክሙ እንተ ትረክበክሙ በደኃሪ መዋዕል ።
፪ ወተጋብኡ ወመጽኡ ደቂቁ ለያዕቆብ፣ ወይቤሎሙ ስምዕዎ ስምዕዎ„ ለአቡክሙ።
፫ ሮቤል በኵርየ ኀያል ውእቱ ዘቀዳሚ ወልድየ እኩየ ከነ ወአግዘፈ ክሳዶ ወዕፁብ ገብረ ።

፬ ቄረ ከመ ማይ እስመ ዐርገ ዲበ ምስካበ አቡሁ ወአርኰሰ ለውእቱ ምስካብ ይእተ አሚረ ዘዲቤሁ ዐርገ።
"ሮቤል በኵርየ ርእሰ ጥብዓንየ ጸነ ከመ ማይ ጊዜ
"ስቅየተ ምድር ወበሕቱ ትኀድር ላዕሌሁ ጸጋ እግዚ
"አብሔር እስመ ገብረ ምሕረተ ምስለ ዮሴፍ ወልድየ„።
፭ ስምዖን ወሌዊ አኀው እሙንቱ ፈጸምዋ ለዐመፃ በቃሕዎሙ ወበኲናቶሙ ።

፮ ነፍስየ ኢትትራከበሙ ወኢይረድ ውስተ ሁከቶሙ እስመ በመዐቶሙ ቀተሉ ሰብአ ወበፍትወቶሙ መተሩ ሥርወ አህጉር ።
፯ ርጉመ ለይኩን መዐቶሙ እስመ ኢገገጹ እምቍጥዓሆሙ ወኢተመይጡ እመዓቶሙ እከፍሎ ውስተ ያዕቆብ ወእዘርዎ ውስተ እስራኤል ።
፰ ይሁዳ፣ ይሴብሑከ አኀዊከ፣ እደዊከ ላዕለ ዘባኖሙ ለጸላእትከ፣ ይሰግዱ ለከ ደቂቀ አቡከ ።
፱ ይሁዳ እጓለ አንበሳ እምኀዝአትከ ዕርገ ወልድየ ሰከብከ ወኖምከ ከመ አንበሳ ወከመ እጓለ አንበሳ አልቦ ዘያነቅሖ ።
፲ ኢይጠፍእ ምልክና እምይሁዳ ወሥስፍና እምአባሉ እስከ አመ ይረክብ ዘጽኑሕ ሎቱ ወውእቱ ተስፋሆሙ ለአሕዛብ ።
፲፩ የአስር በዐፀደ ወይን ዕዋሉ ወበዕፀ ዘይት አድጎ ወየሐፅብ በወይን አልባሲሁ ወበደመ አስከል ሰንዱኖ።

፲፪ ፍሡሐት አዕይንቲሁ እምወይን ወፀዓዳ ከመ ሐሊብ ስነኒሁ ።
፲፫ ዛብሎን፣ ሥዑኖ የኃድር ከመ መርሶ አሕማር ወይሰፍሕ እስከ ሲዶና ።
፲፬ ይሳክር፣ ፈተወ ለሠናይት ወየዐርፍ ማእከለ መዋርስት።

፲፭ ወሶበ ርእየ ከመ ሠናይት ይእቲ ዕረፍት አትሐተ መትከፍቶ ከመ ይትቀነይ ለምድር ወኮነ ወከነ ሐረሳዌ ብእሲ ።
፲፮ ዳን፣ ይኴንን ሕዝበ ከመ አሐቲ እምነገደ እስራኤል።
፲፯ ከዋ ለዳን አርዌ ምድር ዘይጸንሕ ውስተ ፍኖት ዘይነ

ምድርም ይመልሱችሁ። ዘፍ፣ ፵፯ ፱ ።
እኔም ከወንድሞችህ የሚበልጥ መልካም ምርኮን እሰጥኻለሁ (ይኸውም) በቀስቴ በጦሬ ከአሞራውያን እጅ ያመጣሁት ነው አለው። ኢያሱ ፳፬ ፴፪ ።

ምዕራፍ ፵፱ ።

ያዕቆብ ልጆቹን ጠርቶ ወደኔ ተሰብሰቡ በኋላ ዘመን የምታገኛችሁን እነግራችኋለሁ አላቸው ።
የያዕቆብ ልጆችም ተሰብስበው መጡ እሱም እንዲህ አላቸው፤ ስሙት አባታችሁን ስሙት አድምጡት ።
የበኩር ልጁ ሮቤል የብርታቴ መገኛ ነበር የበኩር ልጁ ነበር ነገር ግን ክፉ ሆነ አንገቱንም አደነደነ ጭንቅ ነገርንም አደረገ። ዘዳ፣ ፳፩ ፲፯ ። መዝ፣ ፸፰ ፶፩ ።
እንደ ውኃም ሆነ (አይላቅ) ወደ አባቱ መኝታ ወጥቷልና ያንጊዜም የወጣበትን አልጋ አሳድፎታልና ።
"ጨከኜ የረገምሁት ልጄ ሮቤል ምድር ውኃ በምትጠግብበት ጊዜ ወኃው እንዲያዘነብል ወደ ኃጢአት አዘነበለ፤ ነገር ግን የእግዚአብሔር ጸጋ ይደርበት፤
"ለልጄ ለዮሴፍ በጎ ነገር አድርጓልና„።
ወንድማማቾች ስምዖንና ሌዊ በጦራቸውና በፉክራቸው ዓመፅን ፈጸሚት። ዘፍ፣ ፴፱ ፴፫ ።
ሰውነቴ አትገናኛቸው በጥፋታቸውም አልግባ ተቈጥተው ሰውን ገድለዋልና በፈቃዳቸውም የአህጉርን ሥር ቈርጠዋልና። መዝ፣ ፲፯ ፲፱ ። ምሳ፣ ፲፩ ፲፫ ።
ቍጣቸው ርጉም ይሁን ከቍጣቸው አልተመለሱምና ከኩርፍታቸውም ተግ አላሉምና በያዕቆብ እከፍለዋለሁ፣ በእስራኤልም እበትነዋለሁ።
ይሁዳ ወንድሞችህ ያመሰግኑኻል እጆችህ በጠላቶችህ ደንደስ ላይ ናቸው ያባትህ ልጆችም ላንተ ይሰግዱልሃል ።
የይሁዳ አንበሳ ግልገል ከመደብህ ውጣ ልጄ እንደ አንበሳ ተኛህ አንቀላፋህ እንደ አንበሳም ደቦል ሊቀሰቅስህ የሚችል የለም። ዘኍ፣ ፳፫ ፳፬። ዘዳ፣ ፴፫ ፳፪።
መንግሥት ከይሁዳ አይወጣም ምስፍናም ከወገኑ ለእሱ የሚጠበቀውን እስኪያገኝ ድረስ እሱም ለአሕዛብ አለኝታቸው ነው። ዘኍ፣ ፳፬ ፲፯። ዘዳ፣ ፳፰ ፶፯ ።
በወይን ሐረግ ውርጫውን ያስራል፣ አህያይቱንም በዘይት ዛፍ ያስራል ልብሶቹንም በወይን ያጥባል መጐናጸፊያውንም በዘለላው ደም። ዘኍ፣ ፲፫ ፳፫ ።
ዓይኖቹም ከወይን ይልቅ ደስ ያሰኛሉ ጥርሶቹም እንደ ወተት ነጭ ናቸው። መሳ፣ ፳፫ ፳፱ ።
ዛብሎን ጫማውን አዝቦ ይኖራል የመርከቦች ወደብ እንደመሆኑ እስከ ሲዶና ድረስ ይስፋፋል ።
ይሳኮር መልካም ነገርን ወደደ በተወራራሾቹም መከከል ይኖራል። መሳ፣ ፭ ፲፯፣ ፭ ፲፭። መዝ፣ ፷ ፷ ፲፫ ።
ሥራም መልካም እንደሆነች በየጊዜ ምድርን ያርሳት ይቈፍራት ዘንድ ትከሻውን ዝቅ አደረገ ደከመ አራሽ ሰውም ሆነ። ዘፀ፣ ፩ ፲፩። ኢያሱ ፲፯ ፲።
ዳን ከእስራኤል ነገድ እንደ አንዲቱ በወገኑ ይፈርዳል።
ለዳን በመንገድ ላይ የሚያደባ እባብ ተሰጠው የፈረ

ስኩ ሰኰናሁ ለፈረስ ወይወድቅ ዘይጼዐኖ ድኅሬሁ ።

፲፰ ወይጸንሕ ከመ ያድኅኖ እግዚአብሔር ።
፲፱ ጋድ፣ ፈያት ፈየትዎ፣ ውእቱኒ ፈየቶሙ ተሊዎ
ኪሰሮሙ ።
፳ አሴር፣ ጽጉብ እክል ወውእቱ ይሁብ ሲሳየ ለመ
ላእክት ።
፳፩ ንፍታሌም፣ በቀልት ዕፍረት እንተ ትሜኒ አውዕእት
እክለ ።
፳፪ ወልድ ዘይልህቅ ውእቱ ዮሴፍ ወልድየ ዘይልህቅኒ
ወዘይቀንእ ሊተ ወልድየ ወሬዛ ዘይገብእ ኀቤየ ።
፳፫ እለ ጸአልዎ በምክሮሙ ወክንዎ አጋእዝተ ወነደፍዎ።
፳፬ ወተቀጥቀጡ አቅስስቲሆሙ በኀይል ወደክመ ሥርወ
መዝራእተ እደዊሆሙ በእደ ኀይሉ ለያዕቆብ፣ በህየ አጽ
ንዖ ለእስራኤል በኀበ አምላኩ ለአቡከ ።
፳፭ ወረድአከ አምላከ ዚአየ ወባረከከ በበረከተ ሰማይ
እምላዕሉ፣ ወበበረከተ ምድር እንተ ባቲ ኵሉ በበረከተ
አጥባት ወማኅፀን ።
፳፮ በበረከተ አቡከ ወእምከ ጽኑዓን፣ ወእምበረከቶሙ
ለአድባር እለ ውዱዳን ወበረከተ መላእክቲሁ ለእግዚአብ
ሔር ተሀሉ ዲበ ርእሱ ለዮሴፍ ወዲበ ርእሶሙ ለእለ
ክንዎ አኀዊሁ ።
፳፯ ብንያም፣ ተኵላ መሣጢ ይበልዕ በነግህ ወፍና ሠርክ
ይሁብ ሲሳየ ለሕዝብ ።
፳፰ እሉ እሙንቱ ደቂቁ ለያዕቆብ ዐሠርቱ ወክልኤቱ፣
ወዘንተ ነገረ ነገሮሙ አቡሆሙ ወባረኮሙ ለለ አሐዱ
በከመ በረከቱ ።
፳፱ ባረኮሙ ወይቤሎሙ ናሁ አሐውር እንስ ኀበ ሕዝብየ
ወቅብሩኒ ምስለ አበውየ ውስተ በዐት እንተ ሀለወት ው
ስተ ገራህቱ ለኤፍሮን ኬጥያዊ ።
፴ ውስተ በዐተ ክዕበት እንተ አንጻረ ምንባሬ ውስተ
ምድረ ከነአን እንተ ተሣየጣ አብርሃም እምኀበ ኤፍሮን
ኬጥያዊ ለመቃብር ።
፴፩ ህየ ቀበርዎ ለአብርሃም ወለሣራ ብእሲቱ ወበህየ ቀበ
ርዎሙ ለይስሐቅ ወለርብቃ ብእሲቱ ።
፴፪ ወበህየ ቀበርክዋ ለልያሂ ውስተ በዐተ ገራህት እንተ
ተሣየጡ እምኀበ ደቂቀ ኬጢ ።
፴፫ ወአኅሊቆ ያዕቆብ አዝዞቶሙ ለደቂቁ ሰፍሐ እደዊሁ
ወእገሪሁ ዲበ ምስካቢሁ ወሞተ ወተወስከ ኀበ ሕዝቡ ።

ምዕራፍ ፶።

፩ ወወድቀ ዮሴፍ ቅድመ ገጸ አቡሁ ወበከየ ላዕሌሁ
ወሰዓሞ ።
፪ ወአዘዞሙ ዮሴፍ ለአግብርቲሁ እለ ይቀርቡ ኀቤሁ
ያምዕዝዎ ለአቡሁ ወአምዐዝዎ ለእስራኤል እለ ያምዕዙ።

፫ ወፈጸሙ ሎቱ አርብዐ ጽባሐ እስመ ከማሁ ይኁልቁ
መዋዕለ በዘያምዕዙ ወለሀዉዎ ሰብአ ግብጽ ሰብዓ መዋዕለ።

ሱንም ሰኰና ይነክሳል በላዩ ላይ የተቀመጠውም ወደ
ኋላው ይወድቃል ።
እግዚአብሔርም ያድነው ዘንድ ይጠብቀዋል ።
ጋድን ወንበዴዎች ቀሙት እሱም ፍለጋቸውን ተከ
ትሎ ቀማቸው። ዘፍ፣ ፴ ፲፩ ።
አሴር እኽልን የጠገበ ነው እሱም ለአለቆች ምግብ
ይሰጣል ።
ንፍታሌም ዘኁበበ ነው የምታምርም ሽቱ ዘላላን
አወጣች ።
ዮሴፍ ታዳጊ ልጅ ነው፣ የሚበልጠኝ ልጄ ለኔም የሚ
ቀና ከሞተ በኋላ የተመለሰልኝ ጐልማሳው ልጄ ።
ተማክረው የሰደቡት ጌቶች የሆኑት ይወጉት ነበር።
ቀስቶቻቸው በኃይል ተቀጠቀጡ ያዕቆብን ከአበረ
ታው እጅም ክንዳቸው ዛለ፣ እስራኤልን በከነዓን ያጸናው
የአባትህ ፈጣሪ አንተንም በግብጽ አገር አጸናህ ።
የኔ ፈጣሪ ረዳህ፣ ከላይ ከሰማይ በሚገኝ በረከት እስ
በረህ ሁሉ በሚገኝበት በምድርም በረከት፣ ከማኅፀንና
ከጡት በሚገኝ በረከት ያክብርህ። ዘፍ፣ ፴፫ ፫ ።
ጽኑዓን በሆኑት በናትህና በአባትህ በረከት፣ ጽኑዓን
ከሚሆኑ ተራሮች (አብርሃምና ይስሐቅ) በሚገኝ በረከት
ያክብርህ፣ የእግዚአብሔር መላእክት በረከት በዮሴፍ ራስ
ላይ ይደር፣ ወንድሞቹም በሆኑት ራስ ላይ (ይደር)።
ብንያም፣ ነጣቂ ተኵላ ነው፣ ምግቡን በጧት ይበላል
ማታ ጊዜም ለሌሎቹ ያከፍላል ። ሕዝቅ፣ ፳፱ ፳፮ ።
አሥራ ሁለቱ የያዕቆብ ልጆች እነዚህ ናቸው፤ አባታ
ቸውም ይህንን ነገር ነገራቸው፤ እያንዳንዱን አባታቸው
በረከቸው፣ እያንዳንዱንም እንደ በረከቱ በረከቸው።
እንዲህም አላቸው፤ እነሆ እኔ ወደ ወገኖቼ እሄዳለሁ
በኬጥያዊው በኤፍሮን እርሻ ውስጥ ባለችው ዋሻ ከአባ
ቶቼ ጋር ቅበሩኝ። ዘፍ፣ ፵፱ ፴፫ ።
አብርሃም ከኬጥያዊው ከኤፍሮን ለመቃብር በገዛት
በከነዓን ምድር በመምሬ አንፃር ባለችው ድርብ ዋሻ።

አብርሃምን በዚያ ቀበሩት ሚስቱ ሣራንም ይስሐ
ቅንና ሚስቱ ርብቃንም በዚያ ቀበሩዋቸው ።
እኔም ልያን ከኬጢ ልጆች በገዟት ድርብ ዋሻ
ቀበርኳት ።
ያዕቆብም ልጆቹን አዝዞ ከጨረሰ በኋላ በመኝታው
ላይ እግሮቹንና እጆቹን ዘርግቶ ሞተ፣ ወደ ወገኖቹም
ተጨመረ። ዘፍ፣ ፵፱ ፳፱ ።

ምዕራፍ ፶።

ዮሴፍ በአባቱ ፊት ላይ ወድቆ አለቀሰ ሳመውም ።

ዮሴፍም ወደሱ የሚቀርቡ ባሮቹን አባቱን ሽቱ ይቀ
ቡት ዘንድ አዘዛቸው፣ ሽቱ የሚቀቡ ሰዎችም እስራኤልን
ሽቱ ቀቡት። ሉቃ፣ ፳፫ ፶፮። ዮሐ፣ ፲፱ ፵።
አርባ ቀንም ፈጸሙለት ሽቱ የሚቀቡበትን ወራት እንዲ
ሁ ይቈጥሩ ነበርና የግብጽም ሰዎች ሰባ ቀን አለቀሱለት።

፬ ወእምድኅረ ተፈጸመ መዋዕለ ላሁ ይቤሎሙ ዮሴፍ ለኀያላነ ፈርዖን እንዘ ይብል እመ ረከብኩ ሞገሰ በቅድሜክሙ ንግርዎ ለፈርዖን በእንቲአየ ።

፭ ወበልዎ አቡየ አምሐለኒ ዘእንበለ ይሙት ወይቤለኒ ውስተ መቃብር ዘከረይኩ ሊተ በምድረ ከነአን ህየ ቅብረኒ ወይእዜኒ እዕርግ ወእቅብሮ ለአቡየ ወእግባእ ።

፮ ወነገርዎ ለፈርዖን፤ ወይቤሎ ፈርዖን ዕርግ ወቅብሮ ለአቡከ በከመ አምሐለከ ።

፯ ወዐርገ ዮሴፍ ይቅብሮ ለአቡሁ ወዐርጉ ምስሌሁ ኵሎሙ ደቀ ፈርዖን ወኵሎሙ ዐበይተ ግብጽ ።

፰ ወኵሉ ሰብአ ቤቱ ለዮሴፍ ወኵሉ አኀዊሁ ወኵሉ ሰብአ ቤቱ ለአቡሁ ወሕፃናቲሆሙሰ ወአባግዒሆሙ ወአልሕምቲሆሙ ኀደጉ ውስተ ምድረ ጌሴም ።

፱ ወአዕረገ ምስሌሁ ሠረገላተ ወአፍራሰ ወኮነ ትእይንቶሙ ዐቢየ ጥቀ ።

፲ ወበጽሑ ኀበ ዐውደ እክል ዘአጣድ ዘሀሎ ማዕዶተ ዮርዳኖስ ወበከይዎ ዐቢየ ብካየ፤ ወጽኑዐ ጥቀ ላሁ ገብሩ ለአቡሆሙ ሰቡዐ መዋዕለ ።

፲፩ ወርእዩ እለ ይነብሩ ውስተ ምድረ ከነአን ውእተ ላሀ በኀበ ዐውደ እክል ዘአጣድ ወይቤሉ ከመዝኑ ላሀ ዘግብጽ ዐቢይ ወበእንተዝ ሰመይዎ ስሞ ላሀ ግብጽ በማዕዶተ ዮርዳኖስ ።

፲፪ ወከመዝ ገብሩ ሎቱ ደቂቁ ።

፲፫ ወአግብእዎ ውስተ ምድረ ከነአን ወቀበርዎ ውስተ በዐት እንተ ተሣየጠ አብርሃም ለመቃብር እምኀበ ኤፍሮን ኬጥያዊ እንተ አንጻረ ምንባሬ ።

፲፬ ወገብአ ዮሴፍ ውስተ ግብጽ ውእቱ ወኵሎሙ እለ ዐርጉ ምስሌሁ ኀቡረ ይቅብርዎ ለአቡሆሙ ወአኀዊሁኒ ።

፲፭ ወእምዝ ሶበ ርእዩ አኀዊሁ ከመ ሞተ አቡሆሙ፤ ይቤሉ ዮጊ ይዜክር ብነ ዮሴፍ እኪተ እንተ ገበርነ ላዕሌሁ ወያገብእ ለነ ፍዳሃ ለኵላ እኪት እንተ አርአይናሁ ።

፲፮ ወመጽኡ ኀበ ዮሴፍ አኀዊሁ ወይቤልዎ አቡከ አምሐሎ አምሐለነ ዘእንበለ ይሙት ።

፲፯ ወይቤ ከመዝ በልዎ ለዮሴፍ ኅድግ ሎሙ አበሳሆሙ ወጌጋዮሙ እስመ እኪተ አርአዩከ ወይእዜኒ ሥረይ ሎሙ ኀጢአቶሙ ለአግብርቲከ በአምላክሙ ለአበዊከ፤ ወበከየ ዮሴፍ እንዘ ይትናገርዎ ።

፲፰ ወመጽኡ ኀቤሁ ወይቤልዎ ናሁ ክነ ንሕነ ለከ አግብርተ ።

፲፱ ወይቤሎሙ ዮሴፍ ኢትፍርሁ እስመ እምእግዚአብሔር ክነ ።

፳ አንትሙሰ መከርክሙ እኪተ ላዕሌየ ወእግዚአብሔር ባሕቱ መከረ ሠናይተ ላዕሌየ ከመ ይኩን ዮም በዘይሴሰይ ሕዝብ ብዙኅ ።

፳፩ ወይቤሎሙ ኢትፍርሁ አነ እሴስየክሙ ወለቤትክሙኒ ወፀውዖሙ ወተናገሮሙ ዘይበውእ ውስተ ልቦሙ ።

የልቅሶም ወራት ከተፈጸመ በኋላ ዮሴፍ የፈርዖን መኳንንት እንዲህ አላቸው፤ በፊታችሁ ሞገስ አግኝቼ እንደሆነ የኔን ነገር ለፈርዖን ንገሩት። ዘፍ፡ ፵፯ ፳፱ ።

እንዲህ በሉት፤ አባቴ በከነዓን ምድር ለእኔ በቆፈርኩት መቃብር በዚያ ቅበረኝ ብሎ ሳይሞት አምሎኛል፤ አሁንም ወጥቼ አባቴን ቀብሬ ልመለስ ።

እነሱም ለፈርዖን ነገሩት፤ ፈርዖንም እንደ አማለህ ወጥተህ አባትህን ቀብረው አለው ። ፩ ዜና መዋ፡ ፲፮ ፲፬።

ዮሴፍም አባቱን ይቀብረው ዘንድ ወጣ፤ የፈርዖን አሽከሮችም ሁሉ አብረዉት ወጡ፤ የግብጽ መኳንንቶችም ሁሉ ።

የዮሴፍ ቤተ ሰቦችም ሁሉ ወንድሞቹም ሁሉ የአባቱም ቤተ ሰቦች ሁሉ ከሱ ጋራ ወጡ፤ ልጆቻቸውን ላሞቻቸውንና በጎቻቸውን ግን በጌሴም ምድር ተዉ ።

ከሱም ጋራ ፈረሰኞችንና ሠረገላዎችን አወጣ፤ ሰፈራቸውም እጅግ ሰፊ ሆነ ። ዘፍ፡ ፵፭ ፲ ።

በዮርዳኖስ ማዶ ወደ አለ ወደ አጣድ እኽል አውድማ ደርሰው ጽኑ ልቅሶን አለቀሱለት፤ ለአባታቸውም ሰባት ቀን እጅግ ብርቱ ኃዘን አደረጉ ።

በከነዓን የሚኖሩ ሰዎችም በአጣድ የእኽል አውድማ የሆነውን ያንን ልቅሶ አይተው የግብጽ ልቅሶ እንዲህ የጸና ነውን! አሉ፤ ስለዚህም ስሙን የግብጽ ልቅሶ ብለው ጠሩት፤ እርሱም በዮርዳኖስ ማዶ ነው ።

ልጆቹም እንዲህ አደረጉለት ።

አምጥተው አብርሃም ከኬጥያዊው ከኤፍሮን ለመቃብር በገዛት በመሰብሰቢያው ዘፍ አንፃር ባለችው ዋሻ ቀበሩት ። ግ፡ ሐ፡ ፯ ፲፮ ።

ዮሴፍም ወደ ግብጽ ተመለሰ፤ እሱና አባታቸውን ይቀብሩት ዘንድ ከሱ ጋራ አንድነት የወጡትም ወንድሞቹ ሁሉ ተመለሱ ።

ከዚህም በኋላ ወንድሞቹ አባታቸው እንደሞተ በዩ ጊዜ እንዲህ አሉ፤ ምናልባት እነሆ ዮሴፍ በርሱ ላይ ያደረግነውን ክፋት አስበ ያሳየነውን ክፋት ሁሉ ብድራቱን ይመልስብን ይሆን፤ አሉ ። ዘፍ፡ ፵፱ ፳፫ ።

ወንድሞቹም ወደ ዮሴፍ መጥተው እንዲህ አሉት፤ አባትህ ሳይሞት መሐላን አምሎናል ። ዘፍ፡ ፲፯ ፲፰ ።

እንዲህ ብሎ ዮሴፍን እንዲህ በሉት፤ መከራ አሳይተዉኻልና ኃጢአታቸውን በደላቸውን ይቅር በላቸው አሁንም ስለ አባቶችህ አምላክ ብለህ የባሮችህን ኃጢአት ይቅር በል ዮሴፍም እንዲህ ሲሉት አለቀሰ ።

ወደ እርሱም መጥተው እነሆ እኛ ላንተ ተገዥዎች ሆነናል አሉት ።

ዮሴፍም እንዲህ አላቸው፤ ይህ ነገር ከእግዚአብሔር ታዞ ሆኖአልና አትፍሩ አላቸው ። ፩ ነገ፡ ፭ ፯ ።

እናንተስ በኔ ላይ ክፉ ነገር መክራችሁ ነበር፤ እግዚአብሔር ግን በእኔ ላይ መልካም ነገር አደረገ፤ ዛሬ ብዙ ሕዝብ ምግብ እንዲያገኝ ይሆን ዘንድ ።

አትፍሩ እናንተንም ቤተ ሰቦቻችሁንም እኔ እመግባችኋለሁ ብሎ አጽናናቸው ጠ፡ቶም ከልባቸው የሚገባውንነገራቸው

፳፪ ወነበረ ዮሴፍ ውስተ ግብጽ ውእቱ ወአኅዊሁ ወኵሉ ቤተ አቡሁ፤ ወሐይወ ዮሴፍ ምእተ ወዐሠርተ ዓመተ።
፳፫ ወርእየ ዮሴፍ ደቂቀ ኤፍሬም እስከ ሣልስ ትውልድ ወደቂቀ ማኪር ወልደ ምናሴ እለ ተወልዱ ላዕለ ሕፅነ ዮሴፍ።
፳፬ ወይቤሎሙ ዮሴፍ ለአኅዊሁ አንሰ እመውት ወእግዚአብሔር ይሔውጸክሙ ወያወፅአክሙ እምዛቲ ምድር ወያበውአክሙ ውስተ ምድር ዘመሐለ ለአበዊነ አብርሃም ይስሐቅ ወያዕቆብ።
፳፭ ወአምሐሎሙ ዮሴፍ ለደቂቀ እስራኤል ወይቤሎሙ አመ ይሔውጸክሙ እግዚአብሔር አውፅኡ አዕፅምትየ እምዝየ ምስሌክሙ።
፳፮ ወሞተ ዮሴፍ በምእት ወዐሠርቱ ዓመት፤ ወአምዐዝዎ ወሤምዎ በነፍቅ ውስተ ብሔረ ግብጽ።

ዮሴፍም በግብጽ ኖረ እሱ ወንድሞቹም ያባቱም ቤተ ሰቦች ሁሉ፤ ዮሴፍም፻መቶ አሥር ዓመት ኖረ።
ዮሴፍ የኤፍሬምን ልጆች እስከ ሦስት ትውልድ ድረስ አየ፤ በዮሴፍ ጕልበት ላይ ያደጉትን የምናሴ ልጅ የማኪርንም ልጆች አየ። ዘኍ፣ ፴፪ ፴፱። ሩት፣ ፬ ፲፯።
ዮሴፍም ወንድሞቹን እንዲህ አላቸው፤ እኔ እሞታለሁ እግዚአብሔርም (በረድኤት) ይጎበኛችኋል ከዚችም ምድር ያወጣችኋል ለአበቶቻችን ለአብርሃም ለይስሐቅ ለያዕቆብ ወደ ማለላቸው ምድር ወደ ከነዓን ያገባችኋል።
ዮሴፍም የያዕቆብን ልጆች እግዚአብሔር በጎበኛችሁ ጊዜ አጥንቴን ከዚህ ከግብጽ ከናንተ ጋራ አውጡ ብሎ አማላቸው። ዘጸ፣ ፲፫ ፲፱። ኢያሱ ፳፬ ፴፪።
ዮሴፍም በ፻፲ ዓመቱ ሞተ፤ ሽቱም ቀብተው በሣጥን አድርገው በግብጽ አገር አኖሩት።

ተፈጸመ ኦሪት ዘልደት
ወስብሐት ለእግዚአብሔር ፈጣሬ ኵሉ ፍጥረት
አሜን።

ተፈጸመ ኦሪት ዘልደት
ለእግዚአብሔር ክብር ምስጋና ይግባው በእውነት
አሜን።



# ኦሪት ዘፀአት

| ምዕራፍ ፩ ። | | ምዕራፍ ፩ ። |
|---|---|---|
| ዝ ውእቱ አስማቲሆሙ ለደቂቀ እስራኤል እለ በኡ ብሔረ ግብጽ ምስለ ያዕቆብ አቡሆሙ ብእሲ ብእሲ ወቤቱ። | ፩ | አንዱም አንዱም ሰው ወገኑን ከአባታቸው ከያዕቆብ ጋር ወደ ግብጽ አገር የገቡ የያዕቆብ ልጆች ስማቸው ይህ ነው ፤ ዘፍ፥ ፵፮ ፰ ። ዘፀ ፥ ፮ ፲፬ ። |
| ሮቤል ፥ ወስምዖን ፥ ወሌዊ ፥ ወይሁዳ ። | ፪ | ሮቤል ፥ ስምዖን ፥ ሌዊና ይሁዳ ። |
| ይሳኮር ፥ ወዛብሎን ፥ ወዳን ። | ፫ | ይሳኮር ፥ ዛብሎንና ዳን ። |
| ንፍታሌም ወጋድ ወአሴር ወብንያም ። | ፬ | ንፍታሌም ፥ ጋድ ፥ አሴርና ብንያም ናቸው ። |
| ወዮሴፍሰ ሀሎ ብሔረ ግብጽ ወኮነት ኵላ ነፍስ እንተ እምያዕቆብ ሰብዓ ። | ፭ | ዮሴፍ ግን (ከወንድሞቹ ተለይቶ) በግብጽ አገር ይኖር ነበር ፥ ከያዕቆብ ጋራ ወደ ግብጽ የወረደች ሰውነት ሁሉ ሰባ ናት ። ዘፍ፥ ፵፮ ፳፯ ። ዘዳ፥ ፲ ፳፪ ። |
| ወሞተ ዮሴፍ ወኵሉ አኀዊሁ ወኵሉ ውእቱ ትውልድ። | ፮ | ዮሴፍ ሞተ ፥ ወንድሞቹም ሁሉ ሞቱ ፥ ይህም ትውልድ ሁሉ ወገን ሞቱ ። ዘፍ፥ ፶ ፳፮ ። |
| ወበዝኁ ደቂቀ እስራኤል ወመልኡ ወኮኑ ሕቊራነ ወጸንዑ ጥቀ ዐቢዘ ወመልአት ምድር እምኔሆሙ ። | ፯ | የእስራኤል ልጆች በዝተው (አገሩን ሁሉ) ሞሉት ፥ በግብጻውያንም ዘንድ የተጠሉ ሆኑ ፥ እጅግም በረቱ ፥ ከብዛታቸውም የተነሣ ምድር መላች ። ዘፍ፥ ፩ ፩ ፳፰ ። |
| ወተንሥአ ካልእ ንጉሥ ዲበ ግብጽ ዘኢየአምሮ ለዮሴፍ ። | ፰ | በግብጽም ዮሴፍን የማያውቀው ሌላ ንጉሥ ተነሣ ። ዘፀ ፥ ፪ ፳፫ ። ግብ፥ ሐዋ፥ ፯ ፲፰ ። |
| ወይቤሎሙ ለሕዝቡ ናሁ ሕዝበ ደቂቀ እስራኤል ዐቢይ ወብዙኃ ወይጸንዑነ ። | ፱ | ሕዝቡንም እንዲህ አላቸው ፤ የእስራኤል ልጆች ወገኖች እነሆ ፈጽመው በዙ በኛም ይጸኑብናል ። |
| ንዑ ንጠበቦሙ እስመ እምከመ በዝኁ ወእምከመ በጽሐነ ፀብእ ይትዌሰኩ እሉኒ ዲበ ፀርነ ወይፀብኡነ እምድኅሬነ ወያወጽኡነ እምድርነ ። | ፲ | ከበዙም ሰልፍ በደረሰብን ጊዜ እሊህ ከጠላቶቻችን ጋር ተጨምረው በኋላችን ተከትለው ይወጉናል ፥ ከአገራችንም ያወጡናልና ኑ እንጠበብባቸው አላቸው ። |
| ወሤሙ ዲቤሆሙ ሊቃነ ግብር ከመ ይሣቅዩዎሙ በግብር ፥ ወነደቁ አህጉረ ጽኑዓተ ለፈርዖን ፊቶም ወራምሴ ወኦን እንተ ይእቲ ሀገረ ፀሐይ ። | ፲፩ | በሥራም መከራ ያጸኑባቸው ዘንድ በላያቸው የሠራተኞች አለቆችን ሾሙ ፥ ለፈርዖንም የጸኑ አምባዎችን ሠሩ (እሊህም) ፊቶም ራምሴና ዖን ናቸው ፥ ይህችም ኦን ፀሐይ የፀናባት አገር ናት ። ዘፍ፥ ፲፭ ፲፫ ። ዘፀ ፥ ፫ ፯ ። |
| ወበአምጣነ ይሣቅይዎሙ ከማሁ ይበዝኁ ወይጸንዑ። | ፲፪ | ነገር ግን መከራ በሚያጸኑባቸው መጠን ይበዙም ይጸኑም ነበር ። ዘፍ፥ ፳፰ ፲፬ ። ፳፪ ፫ ። |
| ወያስቆርርዎሙ ግብጽ ለደቂቀ እስራኤል ወይቀንይዎሙ በሥቃይ ። | ፲፫ | የግብጽም ሰዎች የእስራኤልን ልጆች ይጸየፉዋቸው ነበር ፥ በመከራም ይገዙዋቸው ነበር ። |
| ወያጼዕሩ ሕይወተ ነፍሶሙ በግብር ዕፁብ ወበግንፋል ወበዕቡር ወበኵሉ ግብረ ሐቅል ወበኵሉ ግብር ዘይቀንይዎሙ በሥቃይ ። | ፲፬ | ሰውነታቸውንም በጭንቅ ሥራ ጡብ በማስጣል ፥ ጭቃን በማስላቆጥ ፥ ኖራን በማስወገጥ በእርሻም ሥራ ሁሉ ያስጨንቁዋት ነበር ፥ የሚገዙዋቸውም በሥራ ሁሉ የሚያስጨንቅ ነበር ። |
| ወይቤሎን ንጉሠ ግብጽ ለመወልዳተ ዕብራውያት ስማ ለአሐቲ ሲፓራ ወስመ ካልእታ ፎሐ ። | ፲፭ | የግብጽም ንጉሥ አንዲቱ ስሟ ሲፓራ የሁለተኛይቱም ስም ፎሐ የሚባል የዕብራውያት አዋላጆችን ። |
| ሶበ ታወልዳሆን ለዕብራውያት እምከመ በጽሐት ለወሊድ እመ ተባዕት ውእቱ ቅትላሁ ወእመሰ ወለት ይእቲ አሕይዋሃ ። | ፲፮ | ዕብራውያትን በምታዋልዱዋቸው ጊዜ ወንድ ልጅ ቢሆን ግደሉት ፥ ሴት ልጅ ብትሆን ግን አድኗት አላቸው ። |
| ወፈርሃሁ ለእግዚአብሔር እልኩ መወልዳት ወኢገ | ፲፯ | እሊያ አዋላጆች ግን እግዚአብሔርን ፈርተውት |

ብሩ በከመ አዘዞን ንጉሠ ግብጽ ወአሕየዎ ተባዕተ ።

፲፰ ወጸውዖን ንጉሠ ግብጽ ለመወልዳት ወይቤሎን እፎኑ ተገብራ ከመዝ ወታሐይዋ ተባዕተ ።
፲፱ ወይቤላሁ መወልዳት ለፈርዖን አኮ ከመ አንስተ ግብ ጽ ዕብራውያት አላ እንበለ ትምጻእ መወልዲት ይወልዳ።

፳ ወአሠነየ እግዚአብሔር ለመወልዳት ።
፳፩ ወመጽኡ ሕዝብ ወጸንዑ ጥቀ እስመ ፈርሃ ለእግዚ አብሔር መወልዳት ወገብረ ሎን ዐቢያተ ።
፳፪ ወአዘዞሙ ፈርዖን ለኵሉ ሕዝቡ ወይቤሎሙ ለኵሉ ተባዕት ዘይትወለድ ለዕብራውያን ገርም ውስተ ተከዚ ወኵሎ አንስተ አሕይዉ ።

ምዕራፍ ፪ ።

፩ ወሀሎ አሐዱ ብእሲ እምነገደ ሌዊ ዘስሙ እንበረም ዘነሥአ ሎቱ እምእዋልደ ሌዊ ብእሲተ ።
፪ ወፀንሰት ወወለደት ተባዕተ ወሶበ ርእይዎ ከመ ሠናይ ውእቱ አንበርዎ ሠለስተ አውራኀ ።
፫ ወሶበ ስእኑ እንከ ኀቢኦቶ ነሥአት እሙ ነፍቀ ወቀብዖ አስፈልጦ ወፒሳ ወወደየቶ ለውእቱ ሕፃን ውስቴታ ወሤመቶ ውስተ ማዕዶት ኀበ ተከዚ ።

፬ ወትሔውጽ እኅቱ እምርኁቅ ከመ ታእምር ምንተ ይበጽሖ ።
፭ ወወረደት ወለተ ፈርዖን ትትሐፀብ በውስተ ተከዚ ፡ ወአንስትያ አዋልዲሃ ኀበ ተከዚ ፡ ወሶበ ርእየታ ለይእቲ ነፍቅ ውስተ ማዕዶት ፈነወት ወለታ ወአምጽአታ ።

፮ ወከሠተታ ወርእየት ሕፃነ ይበኪ ውስተ ይእቲ ነፍቅ ወምሀከቶ ወለተ ፈርዖን ወትቤ እምደቂቀ ዕብራውያን ውእቱ ዝ ሕፃን ።
፯ ወትቤላ እኅቱ ለውእቱ ሕፃን ለወለተ ፈርዖን ትፈቅዲኑ እጸውዕ ለኪ ብእሲተ ሐፃኒተ ዕብራዊተ ወትሕፅኖ ለዝ ሕፃን ።
፰ ወትቤላ ወለተ ፈርዖን ሑሪ ፀውዒ ወሐረት እንታክቲ ወለት ወጸውዐታ ለእሙ ለውእቱ ሕፃን ወትቤ ነያ ሐፃኒት።

፱ ወትቤላ ወለተ ፈርዖን ዕቀቢ ሊተ ዘ ሕፃነ ወሐፅኒዮ ፡ ወአነ እሁበኪ ዐስበኪ ፡ ወነሥአቶ ይእቲ ብእሲት ለውእቱ ሕፃን ወሐፀነቶ ።
፲ ወሶበ ጸንዐ ውእቱ ሕፃን ወሰደቶ ኀበ ወለተ ፈርዖን ወኮነ ወልደ ወሰመየቶ ስሞ ሙሴ ፡ ወትቤ እስመ እማይ አውፃእክዎ ።
፲፩ ወኮነ እምድኅረ ብዙኅ መዋዕል ልህቀ ሙሴ ወወፅአ ኀበ አኀዊሁ ወርእየ ሕማሞሙ ወረከበ ብእሴ ግብጻዌ እንዘ ይዘብጦ ለአሐዱ ዕብራዊ እምአኀዊሁ ደቂቀ ፳ኤል።

፲፪ ወነጸረ ለፌ ወለፌ ወአልቦ ዘርእየ ፡ ወቀተሎ ለዝኩ

የግብጽ ንጉሥ እንዳዘዛቸው አላደረጉም ፡ ወንድ ወንዶችን አዳኑ ። ዘፍ፡ ፵፪ ፲፰ ፡ ምሳ፡ ፲፬ ፴፩ ።
የግብጽም ንጉሥ አዋላጆቹን ጠርቶ ለምን እንዲህ ታደርጋላችሁ ወንድ ወንዱን ታድናላችሁ አላቸው ።
አዋላጆቹም ፈርዖንን እንዲህ አሉት ፤ የዕብራውያን ሴቶች እንደ ግብጽ ሴቶች አይደሉም ፡ አዋላጂቱ ሳትመጣ ይወልዳሉ እንጂ ።
እግዚአብሔርም ለአዋላጆቹ በጎ ነገር አደረገላቸው ።
ሕዝቡም በዙ እጅግም ጸኑ (በረቱ) አዋላጆቹም እግ ዚአብሔርን ስለ ፈሩት ታላላቅ ነገር አደረገላቸው ።
ፈርዖንም ወገኖቹን ሁሉ ለዕብራውያን የሚወለደው ወንድ ወንዱን ሁሉ ወደ ወንዝ ጣሉት ፡ ሴት ሴቱን በሕ ይወት ተዉ ፡ (አድኑ) ብሎ አዘዛቸው ።

ምዕራፍ ፪ ።

ከነገደ ሌዊ የተወለደ ከሌዊ ልጆች ሚስት ያገባ ስሙ እንበረም የሚባል አንድ ሰው ነበረ ፡ ዘኁ፡ ፳፮ ፶፱ ።
(እሷም) ፀንሳ ወንድ ልጅ ወለደች ያማረ (የተወደደ) ሁኖ ባየች ጊዜ ሦስት ወር ሸሽገው አኖሩት ።
ከዚህ በኋላ ሠውሮ ማኖር በተሳናቸው ጊዜ እናቱ ሣ ጥን አምጥታ የባሕር አረፋ አዶሮ ማር ፡ ሙጫ አስሰብጣ ያንን ሕፃን በሣፅኑ ውስጥ አድርጋ በወንዙ ዳር አኖረ ችው ። ኢሳ፡ ፲፰ ፪፡ ዘፀ፡ ፪ ፭ ።
እኅቱም ምን እንደ እንደሚደርስበት ታውቅ ዘንድ ሩቅ ሁና ትመለከት ነበር ። ዘኁ፡ ፳፮ ፶፱ ።
የፈርዖን ልጅ (ተርሙት) ልትታጠብ ወደ ወንዝ ወረ ደች ፡ ደንገጥሮቿም በወንዙ ዳር ይመላለሱ ነበር ፡ ያች ንም ሣጥን አሸግራ ባየቻት ጊዜ ብላቴናዋን ልካ አስመ ጣቻት ። ግብ፡ ሐዋ፡ ፯ ፳፩ ።
ሣጥኒቱንም ከፍታ ሕፃኑ በሣጥኒቱ ውስጥ ሲያለቅስ አይታ ፡ ይህ ልጅ ከዕብራውያን ልጆች ይሆናል ብላ ራራችለት ። ዘፀ፡ ፪ ፭ ።
የዚያም ልጅ እኅት (ማርያም) የፈርዖንን ልጅ ያንን ልጅ እንድታሳድጊልሽ ዕብራዊት የምትሆን አሳዳጊ ሴት እጠራልሽ ዘንድ ትወጃለሽን፤ አለቻት ።
የፈርዖንም ልጅ ሂደሽ ጥሪልኝ አለቻት ፡ ያችም ብላቴ ሂዳ የዚያን ልጅ እናት ጠራቻት እነሆም የምታሳድግ ሴት ይህች ናት አለቻት ።
የፈርዖንም ልጅ ይህን ሕፃን ተከባከብሽ አሳድጊልኝ እኔም ደመወዝሽን እሰጥሻለሁ አለቻት ፡ ያችም ሴት ያንን ሕፃን ተቀብላ አሳደገችው ።
ያም ልጅ በደገ ጊዜ ወደ ፈርዖን ልጅ ወሰደችው ፡ ልጅም ሆናት ከውኃ አወጣሁት ስትል ስሙንም ሙሴ አለችው ። ግብ፡ ሐ፡ ፯ ፳፩ ፡ ዕብ፡ ፲፩ ፳፬ ።
ከብዙ ዘመንም በኋላ እንዲህ ሆነ፤ ሙሴ አድጎ ወደ ወንድሞቹ ሄደ ፡ መከራቸውንም አየ ፡ ከወንድሞቹም ከእ ስራኤል ልጆች አንዱን ዕብራዊ አንድ ግብጻዊ ሲመታው አገኘ ። ግብ፡ ሐ፡ ፯ ፳፫ - ፳፬ ።
ወድያና ወዲህም ተመለከተና ያየው ሰው አልነበረም

ግብጻዊ ወደፈኖ ውስተ ኆፃ ።
፲፫ ወወፅአ በሳኒታ ዕለት ወረከበ ክልኤተ እደወ ዕብራ
ውያነ እንዘ ይትበአሱ ወይቤሎ ሙሴ ለዘይገፍዖ ለምንት
ትዘብጦ ለካልእከ ።
፲፬ ወይቤሎ ዝኩ ዘይዔምፆ ለካልኡ መኑ ሤመከ መል
እከ ወመኰንነ ላዕሌነ ፡ አው ትቀትለኒኑ ትፈቅድ በከመ
ቀተልኮ ትማልም ለግብጻዊ ፡ ወፈርሀ ሙሴ ወይቤ ከመ
ዝኑ ክሡተ ኮነ ዝ ነገር ።
፲፭ ወሰምዐ ፈርዖን ዘንተ ነገረ ወፈቀደ ይቅትሎ ለሙሴ
ወተግኅሠ ሙሴ እምገጸ ፈርዖን ወኀደረ ውስተ ምድረ
ምድያም ወሶበ በጽሐ አሐተ ምድረ ምድያም ነበረ ዲበ
ዐዘቅት ።
፲፮ ወቦ ለማርያ ምድያም ሰብዑ አዋልድ ወይርዕያ አባ
ግዐ አቡሆን መጽአ ወሄበ ሎን እስከ መልአ ገብላተ ከመ
ያስትያ አባግዐ አቡሆን ።
፲፯ ወሶበ መጽኡ ኖሎት አሰሰልዎን ወተንሥአ ሙሴ
ወአድኅኖን ወአስተየ አባግዐ ።
፲፰ ወሖራ ኀበ ራጉኤል አቡሆን ወይቤሎን እፎኑ አፍ
ጠንክን መጺአ ዮም ።
፲፱ ወይቤላሁ ብእሲ ግብጻዊ አድኀነነ እምኖሎት ወሄበ
ለነ ወአስተየ አባግዒነ ።
፳ ወይቤሎን ለአዋልዲሁ አይቴ ውእቱ ብእሲሁ ወለም
ንት ኀደጋሁ ለብእሲ ጸውዓሁ ከመ ይብላዕ እክለ ።

፳፩ ወኀደረ ሙሴ ኀበ ውእቱ ብእሲ ወወሀቦ ወለቶ ሲፓ
ራሃ ትኩኖ ብእሲተ ።
፳፪ ወፀንሰት ይእቲ ብእሲት ወወለደት ወልደ ወሰመዮ
ስሞ ሙሴ ጌርሳም ፡ ወይቤ እስመ ነግድ አነ በምድረ
ነኪር ።
፳፫ ወፀንሰት ዳግመ ወወለደት ወልደ ወሰመዮ ኤልዛር ፡
ወይቤ ፈጣሪ ዘአቡየ ረዳእየ ።

፳፬ ወእምድኅረ ብዙኅ መዋዕል ሞተ ንጉሠ ግብጽ ወግ
ዕሩ ደቂቀ እስራኤል እምግብሮሙ ወአውየው ወዐርገ
አውያቶሙ ኀበ እግዚአብሔር እምግብሮሙ ።
፳፭ ወሰምዐ እግዚአብሔር ገዓሮሙ ወተዘከረ መሐላሁ
ዘመሐለ ለአብርሃም ወይስሐቅ ወያዕቆብ ወሐወጾሙ ለደ
ቂቀ እስራኤል ወተአምረ ሎሙ ።

## ምዕራፍ ፫ ።

፩ ወሀሎ ሙሴ ይርዒ አባግዐ ዮቶር ሐሙሁ ማርያ ምድ
ያም ፡ ወወሰደ አባግዒሁ ሐቅለ ወበጽሐ ውስተ ኮሬብ
ደብረ እግዚአብሔር ።
፪ ወአስተርአዮ ለሙሴ መልአከ እግዚአብሔር በነደ
እሳት እምዕፀት ፡ ወርእየ ሙሴ ከመ እምዕፀት ይነድድ
እሳት ወዕፀታ ኢትውዒ ።
፫ ወይቤ ሙሴ እብጻሕ ወእርአይ ዘ ራእየ ዐቢየ እፎ
ኢትውዒ ዛ ዕፀት ።

ያኘን ግብጻዊ ሰው ገድሎ በአሸዋ ውስጥ ቀበረው ።
በበነጋውም ዕለት ወጥቶ ሁለት የዕብራውያን ሰዎች
ሲጣሉ አግኝቶ ሙሴ የሚበድለውን አይቶ ለምን ወንድ
ምህን ትመታዋለህ ፤ አለው ፡ ግብ፡ ሐዋ፡ ፯ ፳፮ ።
ያም ወንድሙን የሚበድለው ሰው በኛ ላይ አለቃ
ዳኛ ፡ አድርጎ የሾመህ ማን ነው ፤ ወይስ የግብጹን ሰው
ትላንትና እንደ ገደልከው ልትገድለኝ ትሻለህን ፤ አለው ፡
ሙሴም ይህ ነገር እንዲህ የተገለጠ ሆኗልን ብሎ ፈራ ።
ፈርዖንም ይህንን ነገር ሰምቶ ሙሴን ሊገድለው ፈለገ
ሙሴም ከፈርዖን ፊት ሸሽቶ በምድያም አገር ተቀመጠ ፡
ከምድያም ወደ አንዲቱ አገር በደረሰም ጊዜ በውኃ ጉድ
ጓድ አጠገብ ተቀመጠ ። ግብ፡ ሐ፡ ፯ ፳፱፡ ዕብ፡ ፲፩ ፳፯።
ለምድያም ካህን ሰባት ሴቶች ልጆች ነበሩት ፡ ያበታ
ቸውን በጎች ይጠብቁ ነበር ፡ መጥተውም ያበታቸውን በጎች
ያጠጡ ዘንድ ገንዳው እስኪሞላ ድረስ ቀዱላቸው ።
እረኞችም መጥተው በከለከሉዋቸው ጊዜ ፡ ሙሴ
ተነሥቶ አዳናቸው ፡ በጎችንም አጠጣ ። ዘፍ፡ ፳፱ ፲ ።
ወዳባታቸው ወደ ራጉኤልም ሄዱ ፡ ዛሬስ እንዴት
ፈጥናችሁ መጣችሁ ፤ አላቸው ። ዘሌ፡ ፲ ፳፱ ።
(እነሱም) አንድ የግብጽ ሰው ከእረኞች አዳነን ውኃ
ውንም ቀድቶ በጎቻችንን አጠጣልን አሉት ።
ልጆቹን ሰውየው የት ነው ፤ (ወዴት አለ) ለምንስ ትታ
ችሁት መጣችሁ ፤ (አሁንም) እንጀራ ይበላ ዘንድ ሰውዩ
ውን ጥሩት አላቸው ። ዘፍ፡ ፴፩ ፶፬ ።
ሙሴም በዚያ ሰው ዘንድ አደረ ፡ ሚስትም ትሆነው
ዘንድ ሲፓራ የተባለች ልጁን ሰጠው ።
ያችም ሴት ፀንሳ ወንድ ልጅ ወለደች ሙሴም ስሙን
ጌርሳም ብሎ ጠራው ፡ እኔ በባዕድ አገር መጻተኛ ነኝ ሲል ።

ዳግመኛም ፀንሳ ወንድ ልጅ ወለደች ያባቴ ፈጣሪ
ረዳኝ ሲል ኤልዛር አለው ፡ (ኤልዛር ማለት የእግዚአብ
ሔር ረድኤት ማለት ነው) ።
ከብዙ ዘመንም በኋላ የግብጽ ንጉሥ ሞተ ፡ የእስኤል
ልጆች ከሥራቸው ብርታት የተነሣ አለቀሱ ፡ ጮኹም ፡
ጩኸታቸውም ወደ እግዚአብሔር ደረሰ ።
እግዚአብሔርም ጩኸታቸውን ሰምቶ ለአብርሃም ለይ
ስሐቅና ለያዕቆብ የማለውን መሐላ አሰበ ፡ (አስቦም) የእስ
ራኤልን ልጆች (በረድኤት) ጐበኛቸው (በረዳትነቱም)
ታወቃላቸው ። ፩ ሳሙ፡ ፩ ፲፩ ፡ ዘዳ፡ ፴፫ ፱ ።

## ምዕራፍ ፫ ።

ሙሴ የአማቱ የምድያም ካህን የዮቶርን በጎች ሲጠ
ብቅ ኖረ ፡ በጎቹንም ወደ በረሓ ወስዶ ወደ እግዚአብሔር
ተራራ ወደ ኮሬብ ደረሰ ። መዝ፡ ፸፴፪ ፪ ።
የእግዚአብሔርም መልአክ ከዕንጨት በወጣው እሳት
ለሙሴ ታየው ፡ ሙሴም ዕንጨትነቷ ሳትቃጠል ከዕንጨ
ትነቷ ወጥቶ እሳት ሲነድ አየ ። ዘዳ፡ ፴፫ ፲፮ ።
ሙሴም ይህች ዕንጨት እንዴት አትቃጠልም ይህን
ደግ ራእይ ከዚያ ደርሼ ልይ አለ ።

፬ ወሶበ ርእዮ እግዚአብሔር ከመ መጽአ ይርአይ ጸውዖ እምዕፀት ወይቤሎ ፤ "ሙሴ ሙሴ" ወይቤ ምንት ውእቱ እግዚኦ ።

እግዚአብሔርም ያይ ዘንድ እንደ መጣ ባየው ጊዜ ከዕንጨቱ ወጥቶ "ሙሴ ሙሴ" ብሎ ጠራው፤ (ሙሴም) አቤቱ ! ምንድር ነው አለ ።

፭ ወይቤሎ ኢትቅረብ ዝየ ፍታሕ አሣእኒከ እምእገሪከ እስመ መካን እንተ አንተ ትቀውም ባቲ ምድር ቅድስት ይእቲ ።

አንተ የቆምክበት ቦታ ክብርት ናትና ወደዚህ አትቅረብ፤ ጫማህንም ከእግርህ አውልቅ አለው ።

፮ ወይቤሎ እግዚአብሔር አነ ውእቱ አምላከ አቡዊከ አምላከ አብርሃም፤ ወአምላከ ይስሐቅ፤ ወአምላከ ያዕቆብ፤ ወሜጠ ገጸ ሙሴ እስመ ፈርሀ ነጽሮ ቅድመ እግዚአብሔር ።

እግዚአብሔር ያባቶችህ የአብርሃም የይስሐቅና የያዕቆብ ፈጣሪ እኔ ነኝ አለው፤ ሙሴም የእግዚአብሔርን ፊት ማየት ፈርቷልና ፊቱን መለሰ (አዞረ) ። ዘፍ፥ ፳፰ ፲፫ ።

፯ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለሙሴ ርእየ ርኢኩ ሥቃዮሙ ለሕዝብየ እለ ውስተ ግብጽ ወአውያቶሙ ሰማዕኩ እምነዳእተ ገባር ።

እግዚአብሔርም ሙሴን በግብጽ ያሉ የወገኖቼን መከራ ማየትን አየሁ፤ ከአስገባሪዎቻቸውም የተነሣ ጩኸታቸውን ሰማሁ አለው ። ዘፀ፥ ፪ ፳፫፤ ነህ፥ ፱ ፱ ።

፰ ወአእመርኩ ጻዕሮሙ ወወረድኩ ከመ አድኅኖሙ እምእደ ግብጽ ወእሰዶሙ ውስተ ምድር ሠናይት ወርኅብት ወአወፅኦሙ እምይእቲ ወአወስዶሙ ውስተ ምድር እንተ ታውኅዝ ሐሊበ ወመዓረ ውስተ ምድሮሙ ለከናኔዎን ወለኬጤዎን ወለአሞሬዎን ወለፌርዜዎን ወለጌርጌሴዎን ወለኤዌዎን ወለኢያቡሴዎን ።

ጭንቀታቸውንም አውቄ ከግብጻውያን እጅ አድናቸው ዘንድ ወደ አማረችና ሰፊም ወደ ሆነች ምድር አወስዳቸው ዘንድ ወረድሁ፤ ከዚያችም ምድር አውጥቼ ማርና ወተትን ወደምታፈሰው (ተድላ ደስታ ወደምታስገኝ) ወደ ከናኔዎንና ኬጤዎን፤ ወደ ኤዌዎንና ወደ ፌርዜዎን ወደ ጌርጌሴዎን ወደ አሞሬዎንና ወደ ኢያቡሴዎን አገር አገባቸዋለሁ ።

፱ ወይእዜኒ ናሁ ገዓሮሙ ለደቂቀ እስራኤል በጽሐ ኀቤየ፤ ወርኢኩ አነ ሥቃዮሙ ዘይሣቅይዎሙ ግብጽ ።

አሁንም እነሆ የእስራኤል ልጆች ጩኸት ወደኔ ደረሰ እኔም የግብጽ ሰዎች የሚያደርሱባቸውን መከራቸውን ተመለከትሁ ። ዘፀ፥ ፪ ፳፫ ።

፲ ወይእዜኒ ነዓ እፈንወከ ኀበ ፈርዖን ንጉሠ ግብጽ ወታወፅኦሙ ለሕዝብየ ደቂቀ እስራኤል እምድረ ግብጽ ።

አሁንም ወደ ግብጽ ንጉሥ ወደ ፈርዖን እልክህ ዘንድ ና፤ የእስራኤል ልጆች ወገኖቼን ከምድረ ግብጽ ታወጣቸዋለህ አለው ።

፲፩ ወይቤሎ ሙሴ ለእግዚአብሔር መኑ አነ ከመ እሖር ኀበ ፈርዖን ንጉሠ ግብጽ ወከመ አውፅኦሙ ለደቂቀ እስራኤል እምድረ ግብጽ ።

ሙሴም እግዚአብሔርን ወደ ግብጽ ንጉሥ ወደ ፈርዖን ሂጄ የእስራኤልን ልጆች ከግብጽ አገር አወጣቸው ዘንድ እኔ ማን ነኝ (ምንድር ነኝ) አለው ።

፲፪ ወይቤሎ እግዚአብሔር እስመ አነ ሀለውኩ ምስሌከ ወዝንቱ ተአምር ለከ፤ ከመ አነ እፌንወከ ሶበ አውጻእኮሙ ለሕዝብየ እምብሔረ ግብጽ ወትፀመድዎ ለእግዚአብሔር በዝ ደብር ።

እግዚአብሔርም እኔ (በረድኤት) ከንተ ጋራ አለሁና፤ እኔም እንደላክሁህ ምልክትህ ይህ ነውና ወገኖቼን ከግብጽ አገር በወጣኻቸው ጊዜ በዚህ ተራራ ለእግዚአብሔር ትገዛላችሁ አለው ። ዘፀ፥ ፲፱ ፫ ።

፲፫ ወይቤሎ ሙሴ ለእግዚአብሔር ናሁ አነ አሐውር ኀበ ደቂቀ እስራኤል ወእብሎሙ አምላከ አበዊክሙ ፈነወኒ ኀቤክሙ ወሶበ ይሴእሉኒ ስሙከ ምንተ እብሎሙ ።

ሙሴም እግዚአብሔርን እንዲህ አለው ፤ እነሆ ወደ እስራኤል ልጆች ሂጄ የአባቶቻችሁ ፈጣሪ ወደናንተ ላከኝ እላቸዋለሁ ነገር ግን ስምህን በጠየቁኝ ጊዜ ምን እላቸዋለሁ ፤ ዘፍ፥ ፴፪ ፳፱ ።

፲፬ ወይቤሎ እግዚአብሔር አነ ውእቱ ዘሀሎ ወይሄሉ ወከመዝ ትብሎሙ ለደቂቀ እስራኤል ዘሀሎ ወይሄሉ ፈነወኒ ኀቤክሙ ።

እግዚአብሔርም ያለና የሚኖር እኔ የእስራኤል ልጆች ቅድመ ዓለም የነበረና ዓለምን አሳልፎ የሚኖር ወደናንተ ላከኝ ትላቸዋለህ አለው ። ዕብ፥ ፲፫ ፰ ።

፲፭ ወዓዲ ይቤሎ እግዚአብሔር ለሙሴ ከመዝ ትብሎሙ ለደቂቀ እስራኤል እግዚአብሔር አምላከ አበዊክሙ ፈነወኒ ኀቤክሙ፤ ዝ ውእቱ ስምየ ዘለዓለም ወዝክርየ ለትውልደ ትውልድ ።

ዳግመኛም እግዚአብሔር ሙሴን የእስራኤል ልጆች እንዲህ ትላቸዋለህ የአባቶቻችሁ ፈጣሪ እግዚአብሔር ወደናንተ ልኮኛል፤ ለዘለዓለም ፀንቶ የሚኖር ስሜ ይህ ነው፤ ስም አጠራሬም ለልጅ ልጅ ነው አለ በላቸው አለው ።

፲፮ ሑር አስተጋብኦሙ ለአእሩገ እስራኤል፤ ወበሎሙ እግዚአብሔር አምላከ አበዊክሙ አምላከ አብርሃም ወአምላከ ይስሐቅ፤ ወአምላከ ያዕቆብ፤ አስተርአየኒ ወፈነወኒ እንዘ ይብል ሐውጾ ሐወጽኩክሙ በእንተ ኵሉ እንተ በጽሐተክሙ በብሔረ ግብጽ ።

ሂድና የእስራኤልን ሽማግሌዎች ሰብስበህ የአባቶቻችሁ የአብርሃም የይስሐቅና የያዕቆብ ፈጣሪ እግዚአብሔር ተገልጾ በግብጽ አገር ስለ ደረሰባችሁ መከራ ሁሉ (በረድኤት) ጐበኘኋችሁ ብሎ ወደናንተ ላከኝ በላቸው ።

፲፯ ወእቤ አነ እነሥአክሙ እምሥቃየ ግብጽ ወአበውአክሙ ውስተ ምድረ ከናኔዎን ወኬጤዎን ወኤዌዎን ወአ

እኔም ተድላ ደስታ ወደምታስገኝ ወደ ከናኔዎን ወደ ኬጤዎን፤ ወደ ኤዌዎንና ወደ አሞሬዎን፤ ወደ ፌርዜዎን

ሞሬዎን ወፌርዜዎን ወጌርጌሴዎን ወኢያቡሴዎን ውስተ
ምድር እንተ ታውኅዝ ሐሊበ ወመዓረ።
፲፰ ወይሰምዑ ቃለከ ወትበውእ አንተ ወአእሩገ እስራ
ኤል ኀበ ንጉሠ ግብጽ ወትብሎ እግዚአብሔር አምላከ
ዕብራውያን ጸውዐነ ንሑር ምሕዋረ ሠሉስ ዕለት ውስተ
ሐቅል ከመ ንሡዕ ለእግዚአብሔር አምላክነ።

፲፱ ወአነ አአምር ከመ ኢያበውሐክሙ ፈርዖን ንጉሠ
ግብጽ ትፃኡ ዘእንበለ በእድ ጽንዕት።
፳ ወእሰፍሕ እዴየ ወእቀትሎሙ ለግብጽ በኵሉ መድም
ምየ ዘእገብር በሙ ወእምድኅረዝ ይፈንወክሙ።

፳፩ ወእሁበሙ ሞገሰ ለሕዝብየ በቅድሜሆሙ ለግብጽ።

፳፪ ወአመ ተሐውሩ ኢትወፅኡ ዕራቃኒክሙ፤ አላ ታስ
ተዋሕስ ብእሲት እምጎራ ወእምኀደርታ ንዋየ ብሩር ወወ
ርቅ ወልብስ፤ ወትወድይዎ በዲበ ደቂቅክሙ ወአዋል
ዲክሙ ወተሐበልይዎሙ ለግብጽ።

ምዕራፍ ፬።

፩ ወአውሥአ ሙሴ ወይቤ ለእመ ኢአምኑኒ ወኢሰ
ምዑ ቃልየ ወይቤሉኒ ኢያስተርአየከ እግዚአብሔር
ምንተ እብሎሙ።
፪ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለሙሴ ምንት ዝ ዘውስተ እ
ዴከ፤ ወይቤ በትር።
፫ ወይቤሎ እግዚአብሔር ግድፎ ውስተ ምድር ወገደፎ
ውስተ ምድር ወኮነ አርዌ ምድር ወጐየ ሙሴ እምኔሁ።
፬ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለሙሴ ስፋሕ እዴከ ወንሥአ
በዘነቡ ወሰፍሐ እዴሁ ሙሴ ወነሥአ በዘነቡ ወኮነ በትረ
ውስተ እዴሁ።
፭ ወይቤሎ ከመ ይእመኑከ ከመ አስተርአየከ እግዚአ
ብሔር አምላከ አበዊሆሙ አምላከ አብርሃም፤ ወአምላከ
ይስሐቅ፤ ወአምላከ ያዕቆብ።
፮ ወይቤሎ ካዕበ እግዚአብሔር ለሙሴ ደይ እዴከ ውስ
ተ ሕፅንከ፤ ወወደየ እዴሁ ሙሴ ውስተ ሕፅኑ፤ ወይቤሎ
አውፅእ እዴከ እምውስተ ሕፅንከ፤ ወአውፅአ እዴሁ እም
ሕፅኑ፤ ወኮነት ፀዓዳ ከመ በረድ ለምጽ።
፯ ወይቤሎ ካዕበ ደይ እዴከ ውስተ ሕፅንከ ወወደየ እ
ዴሁ ውስተ ሕፅኑ ወዓዲ ይቤሎ አውፅእ እዴከ እምሕ
ፅንከ ወአውጽአ እዴሁ እምሕፅኑ ወገብአት ከመ ኆብረ
ሥጋሁ።
፰ ወይቤሎ ለእመ ኢአምኑከ ወኢሰምዑ ቃለከ በተአ
ምር ዘቀዳሚ የአምኑከ በቃለ ተአምሩ ለካልእ።
፱ ወእምከመ ኢአምኑከ በእሉ ክልኤቱ ተአምራት ወኢ
ሰምዑ ቃለከ ትነሥእ እማየ ተከዚ ወትክዑ ውስተ የብስ
ወይከውን ደመ ውስተ የብስ ዝኩ ማይ ዘነሣእከ እም
ተከዚ።
፲ ወይቤሎ ሙሴ ለእግዚአብሔር አስተበቍዕከ እግዚእ

ወደ ጌርጌሴዎን ወደ ኢያቡሴዎን አገር አወጣችኋለሁ
አለ በላቸው። ዘፍ፤ ፶ ፳፬፤ ዘፀ፤ ፬ ፴፩።
ቃልህን ይሰማሉ አንተም ወደ ግብጽ ንጉሥ ትገባ
ለህ የእስራኤልም ሽማግሌዎች ይገባሉ፤ የዕብራውያን ፈ
ጣሪ እግዚአብሔር የሦስት ቀን ጐዳና ሄደን በምድረ በዳ
ለፈጣሪያችን እግዚአብሔር መሥዋዕትን እንሠዋ ዘንድ
ጠርቶናል ትሉታላችሁ። ዘኁ፤ ፳፫ ፫ - ፬፤ ፲፭ ፲፪።
ነገር ግን በጽኑ ሥልጣን ካልሆነ የግብጽ ንጉሥ ፈር
ዖን እንደማያሰናብታችሁ እኔ አውቃለሁ።
እጄን ዘርግቼ (ሥልጣኔን ገልጬ) የግብጽን ሰዎች
በማደርገባቸው ተአምራቴ ሁሉ አጠፋቸዋለሁ፤ ከዚህ
በኋላ ያሰናብታችኋል። ዘፍ፤ ፴፩ ፪፤ ዘዳ፤ ፲፱ ፬።
ለወገኖቼም በግብጻውያን ፊት መወደድን (መፈራትን)
እሰጣቸዋለሁ። ግብ፤ ሐዋ፤ ፯ ፴፯።
በሄዳችሁም ጊዜ በዶዋችሁን አትወጡም (አትሄዱም)
ሴት ከጐረቤቷ ከቤተ ሰቧም የወርቅን የብርን የልብስን
(ጌጣ-ጌጥ) ትዋስ እንጂ በዶአችሁን አትወጡም በወንዶች
ልጆቻችሁና በሴቶች ልጆቻችሁ ላይ ታገቡታላችሁ፤ (በዚ
ህ) የግብጽን ሰዎች ትበዘብዙዋቸው አላችሁ አላቸው።

ምዕራፍ ፬።

ሙሴም ባያምኑኝና ቃሌን በይሰሙ እግዚአብሔርም
አልተነጋገረህም ቢሉኝ ምን እላቸዋለሁ፤ ብሎ መለሰ።

እግዚአብሔርም ሙሴን ይህ በእጅህ የያዝከው ምን
ድር ነው አለው፤ በትር ነው አለው።
እግዚአብሔር በምድር ላይ ጣለው አለው፤ በምድ
ርም ላይ ጣለው፤ በትሩም እባብ ሆነ፤ ሙሴም ከሱ ሸሸ።
እግዚአብሔር ሙሴን እጅህን ዘርግተህ ጅራቱን ያዘ
ው አለው፤ ሙሴም እጁን ዘርግቶ ጅራቱን ይዞ አነሣው
በእጁም እንዳለ በትር ሆነ። ዘፀ፤ ፬ ፲፯።
እግዚአብሔር ያባቶቻቸው የአብርሃም አምላክ የይ
ስሐቅ አምላክ የያዕቆብ ፈጣሪ እንደታየህ እንዲያምኑህ
ጅራቱን ያዘው (በዚህ ያምኑሃል) አለው። ዘፀ፤ ፲፱ ፱።
ዳግመኛም እግዚአብሔር እጅህን ወደ ብብትህ አግባ
አለው፤ ሙሴም እጁን ከብብቱ አገባ፤ እጅህን ከብብትህ
አውጣ አለው፤ እጁን ከብብቱ አወጣ፤ ሁለንትናዋም ነጭ
ለምጽ ሆነች። ዘኁ፤ ፲፪ ፲፤ ፬ ነገ፤ ፭ ፳፯።
ዳግመኛም እጅህን ወደ ብብትህ አግባ አለው፤ እጁ
ን ወደ ብብቱ አገባ፤ ዳግመኛም እጅህን ከብብትህ አውጣ
አለው፤ እጁን ከብብቱ አወጣ የሰውነቱም ኅብረ መልክዕ
እንደ ገላው ኅብር ሆነች።
በፊተኛውም ተአምር ባያምኑህና ቃልህን ባይሰሙ
በሁለተኛው ተአምር ቃል ያምኑሃል።
በነዚህም በሁለቱ ምልክቶች ባያምኑህና ቃልህን ባይ
ሰሙ ከፈሳሹ ውኃ ቀድተህ በደረቁ መሬት ላይ እር
ጨው ይህም ከፈሳሽ ውኃ ቀድተህ የረጨኸው ውኃ
ደም ይሆናል። ዘፀ፤ ፯ ፲፱።
ሙሴም እግዚአብሔርን አቤቱ እለምንሃለሁ፤ ጥንቱ

፲፩ ወትዘብጥ ዕበነ አርባዕ ዘወርቅ ወታነብር ላዕለ አርባዕቱ ምስማካቲሃ፤ ዕበነ ክልኤቱ ውስተ ምስማክ አሐዱ፤ ወዕበነ ክልኤቱ ውስተ ዳግም ምስማክ ።

፲፪ ወግበር ላቲ መገውሪሃ እምዕፀ ዘኢይነቅዝ ወትቀፍሎሙ ወርቀ ።

፲፫ ወታበውእ መገውሪሃ ውስተ ውእቶን ዕበን አርባዕ ዘዲበ ምስማክ ዘታቦት መሰከሚሃ ለታቦት በዘይሰክምዋ በሙ ።

፲፬ ወዕበን ዘዲበ ታቦት ለይኩኑ ድንበዘቲሃ በዘይትዋደዱ ወኢያንቀለቅሉ ።

፲፭ ወግበር ላቲ ተድባበ ዘወርቅ ንጹሕ ዘክዕበ እመት ወመንፈቀ እመት፤ ኑኁ እመት ወመንፈቀ እመት ራኀቡ ።

፲፮ ወግበር ላቲ ክልኤተ ኪሩቤነ ዘወርቅ ፍሑቅ ወትገብሮሙ እምክልኤቱ ምስማካቲሁ ለተድባብ ።

፲፯ ወይትገበር አሐዱ ኪሩብ እምጽንፈ አሐዱ ምስማክ፤ ወአሐዱ ኪሩብ እምጽንፈ ክልእ ምስማክ ።

፲፰ ወግበር ክልኤሆሙ ኪሩበነ ላዕለ ክልኤሆሙ ምስማካት ።

፲፱ ወይኩኑ ኪሩቤን እንዘ ይሬብቡ ክነፊሆሙ እመልዕልተ ተድባብ ወገጾሙ ይትናጸሩ በበይናቲሆሙ ወኀበ ተድባብ ይኩን ገጾሙ ለኪሩቤን ።

፳ ወታነብር ተድባበ ዲበ ታቦት መልዕልቴሃ፤ ወውስተ ታቦት ትወዲ ትእዛዘ ዘአነ እሁበከ ።

፳፩ ወእትኤመር ለከ በህየ ወእትናገረከ እምላዕለ ተድባብ ማእከለ ክልኤቱ ኪሩቤን እለ ሀለዉ ዲበ ታቦት ዘመርጡል ኵሎ ትእዛዘ ዘእኤዝዘከ ኀበ ውሉደ እስራኤል ።

፳፪ ወግበር ማእደ እምዕፀ ዘኢይነቅዝ ኑኁ ክዕበ እመት፤ ወራኀቡ እመት፤ ወቆሙ እመት ወመንፈቀ እመት ።

፳፫ ወትቀፍሎ ወርቀ ንጹሐ ወግበር ሎቱ ቀጸላ በዓውዱ ወግበር ግብረ ማዕበል ዘወርቅ ።

፳፬ ወግበር ክንፈረ መጠነ አርባዕቱ አፃብዕ በዓውዱ ።

፳፭ ወግበር አርባዕተ አውቃፋተ ዘወርቅ ወአንብር ውስተ አርባዕቱ መዓዝኒሁ ለማእድ ።

፳፮ ወይኩኑ አውቃፋት መንገለ ክንፈሩ ለማእድ ።

፳፯ ወይኩኑ አውቃፋቲሁ አብያተ ለመገውሪሁ ዘያነሥኡ ማእደ ።

፳፰ ወግበር መገውሪሁ እምዕፀ ዘኢይነቅዝ ወትቀፍሎሙ ንጹሐ ወርቀ ወበሙ ይትነሣእ ማእዱ ።

፳፱ ወግበር አጽሕልቲሁ ወመጻብሒሁ ወመዳምሂሁ ወመዋጽሒሁ በዘበቱ ታወጽሕ እምንጹሕ ወርቅ ግበሮሙ ።

የወርቁን አራቱን ቀለበት መትተህ በአራት እግሮቿ አኑር፤ ከዚህም ከአራቱ ሁለቱን በአንድ ወገን ሁለቱን በአንድ ወገን አኑረው ።

መሎጊያዎቿን (መሸከሚያዎቿን) ሸዋሸር ሰጢን ከሚባል ከማይነቅዝ ዕንጨት ሥራላት እነዚህንም በወርቅ ለብጣቸው ።

መሸከሚያዎቿንም በሚሸከሙባቸው ገንዘብ ከታቦቱቱ በላይ በአራቱ መዓዝን ወዳሉ ወደ አራቱ ቀለበቶች አግባ ።

በታቦቱቱ ላይ ባሉቱ መዓዝን ባሉ ባራቱ ቀለበቶች (ሌዋውያን) በሚሸከምዋት ገንዘብ የታቦቱቱ ድንበዛት (መሸከሚያዎች) ወለቅ ወለቅ የማይሉ ከላይ እስከታች የተስማሙ ይሁኑ ።

አቈልቋዩ ሁለት ክንድ ከስንዝር፤ ቁመቱ ክንድ ወርዱ ክንድ የሆነ የጸሩ ወርቅ መግጠሚያ ለታቦቱቱ ሥራላት፤ (እንደ አንበር ያለ ነው) ። ፩ ነገ፡ ፰ ፰ ።

ሁለቱንም ኪሩቤል ከለዘበ ከጸሩ ወርቅ ሥራለት፤ ሁለቱንም በመግጠሚያው ላይ ከሁለት ወገን አድርጋቸው።

አንዱ ኪሩብ በአንድ ወገን፤ አንዱም ኪሩብ በአንድ ወገን በመግጠሚያው ላይ ይቀረጹ ።

ሁለቱንም ኪሩቤል በሁለቱ መግጠሚያዎች ላይ አድርጋቸው (ቅረጻቸው) ።

ኪሩቤልም ከላይ ክንፎቻቸውን ዘርግተው ከታቦቱቱ በላይ ያለ መግጠሚያውን ሸፍነው የኪሩቤል ፊታቸው ወደ መግጠሚያው ዘሮ (እንደሚናከሱ ዶሮዎች) እርስ በርሳቸው ፊት ለፊት የሚተያዩ ይሁኑ ።

መግጠሚያውንም በታቦቱቱ ላይ አኑረው፤ ከዚህ በኋላ እኔ የሰጠሁህን ትእዛዝ ዓሠርቱ ቃላት የተጻፉባቸው ሁለቱን ጽላቶች በታቦቱቱ ውስጥ አኑር ።

እኔም በዚያ ሁኜ እገለጽልሃለሁ፤ ለእስራኤል ልጆች ብዬ እኔ የማዝህን ትእዛዝ ሁሉ በታቦቱቱ ላይ ባሉ በሁለቱ ኪሩቤል መካከል ባለ በመግጠሚያው ላይ ሁኜ እነጋገርሃለሁ ። ዘፀ፡ ፳፯ ፴፩፡ ፵ ፳ ።

ከማይነቅዝ ዕንጨት ቁርጠህ ማእድን ሥራ፤ ይኸውም አቈልቋዩ ሁለት ክንድ ወርዱ ክንድ ቁመቱ ክንድ ከስንዝር ነው ። ዘሌ፡ ፲፯ ፬፡ ሕዝ፡ ፱ ፫ ።

በጸሩ ወርቅ ለብጠው በክፈፉ ዙርያም ክንፈር አውጣለት፤ የማይረጋ ወርቅም አድርግበት ።

በዙርያውም አንድ ጋት የሚያህል ክፈፍ አድርግለት።

አራት የወርቅ አምበር ሠርተህ በማእድ ከራት እግሩ በላይ ባለ ከንፈሩ በአራቱ መዓዝኖች አኑረው።

አምበሮቹ በማእዱ ከንፈር ላይ ይሁኑ ።

በማእዱ ከንፈሮች አምበሮችም ማእድን ለሚያነሡ መሸከሚያዎች ቤት ይሁኑ ።

መሸከሚያውንም ሸምሸር ሰጢን ከሚባል ከማይነቅዝ ዕንጨት ሥራ መሸከሚያዎቹንም በጸሩ ወርቅ ለብጣቸው ማእድም በነሱ ይነሣ።

(መጻብሕ) ታላቅ ሥልስ ወጭት (አጽሕልት) ታናሽ ሥልስ ወጭት (መዳምህ) ማንኪያ (መዋጽሕ) ማፍሰሻ ዘይቱን

፴ ወእንብር ኅብስተ ዲበ ማእድ በቅድሜየ ዘልፈ ።

፴፩ ወግበር ተቅዋመ ማኅቶት እምወርቅ ንጹሕ ፍሑቀ ለተቅዋመ ማኅቶት ዓምዳ ወአብራዊሃ ወመአኃዚሃ ፡ ወከበበ ርእሳ ወጽጌያቲሃ እምኔሃ ይትገበሩ ።

፴፪ ወስድስቱ አብራዕ እለ ይትገበራ በገቦሃ ለተቅዋመ ማኅቶት ሠላስ አብራዕ እምአሐዱ ፍናሃ ፡ ወሠላስ አብራዕ እምፍናሃ ካልእ ።

፴፫ ወሠለስቱ መአኃዚሁ እለ የኃብሩ ምሳሌ በአሐዱ ከበበ ርእስ ጽጉይ ከማሁ ለሰብዓቲሆሙ አብራዕ እለ ይወፅኡ እምተቅዋመ ማኅቶት ።

፴፬ ወለተቅዋመ ማኅቶት መአኃዚሃ አርባዕቱ ወጽጌያቲሃ ፤

፴፭ ወከበብ መትሕተ ክልኤቱ አብራዕ ለሰብዓቲሆሙ አብራዕ እለ ይወፅኡ እምተቅዋመ ማኅቶት ።

፴፮ ክበበቲሆሙ ወአብራዊሆሙ እምኔሃ ይኩኑ ኵሎሙ ፍሑቀ እምአሐዱ ወርቅ ንጹሕ ።

፴፯ ወትገብር መኅትዊሃ ሰብዓቱ ወያብርህ እምአሐዱ ገጽ ።

፴፰ ወዘእምድኅሬሃ ወበዘያሜንዋ ወጽዋዓቲሃ ዘወርቅ መክ ሊተ ወርቅ ትገብራ ።

፴፱ ወአላንተ ኵሎን ንዋያቲሃ ግበር በአርአያ ዘከመ አር አይኩክ በደብር ።

ምዕራፍ ፳፮ ።

፩ ወለደብተራ ግበር ላቲ ዐሥርተ አዕጻደ እምቢሶስ ዕፁ ፍ ፡ ወእምኅብረ ያክንት ወእምኅብረ ከብድ ፡ ወለይ ከዑብ ወኪሩቤነ ግበሩ ፡ ወበግብረ ምእናም ትገብርዎ ።

፪ ወኑኁ ለአሐዱ ዓፀድ ዕሥራ ወሰመንቱ በእመት ፡ ወራኅቡ አርባዕቱ በእመት ፡ ለአሐዱ ዐፀድ በመስፈርቱ ከማሁ ለይኩኑ ።

፫ ወኅምስቱ አዕፃድ ይሳመኩ በበናቲሆሙ ።

፬ ወግበር ኵሎሙ ኀምሳ መማስጠ ዘኅብረ ያክንት ላዕለ ከንፈረ አሐዱ ዓፀድ እምአፍአሃ ።

፭ ወኀምሳ መማስጠ ግበር በጽንፈ ካልእ ዐፀድ ፡ እም ገጸ አፍአ ገጸሙ እንዘ ይሳመኩ በበይናቲሆሙ ።

፮ ወግበር ኃምሳ ሮማዳተ ዘወርቅ ወደምር አዕፃዳተ አ ሐዱ ምስለ ካልኡ በሮማዳት ወይኩኑ አሐደ ደብተራ ።

በምታፈስበት ገንዘብ ጽዋዎቹንም ከጸሩ ወርቅ ሥራቸው።
ኅብስቱንም ዘወትር ዘወትር ዘወትር ዘወትር ዘወትር ዘወትር ዘወትር ዘወትር

ዘወትር ጪት ማታ በፊቴ አኑር (ሠዋው)።

፯ ወግበር ዐሥርተ ወአሐደ አዕፃደ ዘሠቅ ዘይከድኖ እምላዕሉ ለደብተራ ።

ድንኳኑን ከላይ እስከ ታች የሚሸፍነው የብስጥ አሥራ አንድ ፈርጅ ሥራ ።

፰ ወለለአሐዱ አሐዱ ሠቅ ኑኁ ሠላሳ በእመት ወራኅቡ ርብዕ በእመት ፡ ከመዝ እምጣኒሆሙ ለዐሠርቱ ወአሐዱ ።

እያንዳንዱም የብስጥ ፈርጅ አቈልቋዩ ሠላሳ ክንድ የወርዱም ስፋት አራት ክንድ የአሥራ አንዱም ፈርጆች መጠናቸው (ልካቸው) እንደዚሁ ነው ።

፱ ወደምር ኃምስተ ሠቃተ በበይናቲሆሙ ወሰብዓተ ሠቃተ ደምር በበይናቲሆሙ ፡ ወተዓፅፍ ሰብዓተ ሠቃተ መንገለ ገጸ ደብተራ ዐሥርተ ።

አምስቱን ፈርጅ ብስጥ እርስ በርሳቸው (በቀለበት) አንድ አድርጋችሁ ሰባቱ ፈርጅ ብስጥም እርስ በርሳቸው እንዲገናኙ አድርግ ፡ ሰባተኛውም ፈርጅ መጋረጃ በድንኳኑ ፊት ይደረብ ።

፲ ወግበር ኃምሳ መማስጠ ላዕለ ከንፈረ አሐዱ ሠቅ ፡ ወኃምሳ መማስጠ ግበር ውስተ ከንፈረ ሠቅ ካልእ በዘትደምር ቀዳማየ ።

አሥሩን ፈርጅ አንድ እንዳደረግኸው በአንድ ብስጥ ፈርጅ ከንፈር ላይ አምሳ ተባት ቍልፍ በሁለተኛውም ብስጥ ፈርጅ ከንፈር ላይ አምሳ ተባት ቍልፍ ሥራ ።

፲፩ ወግበር ኃምሳ ኖፃዳተ ዘብርት ፡ ወትዴምር መማስጠ በኖፃዳት ፡ ወታኀብር ሠቃተ ወይከውኑ አሐደ ።

ከዚህም አምሳ የብርት (የናስ) እንስት ቍልፍ ሥራ ፡ ተባት ቍልፉንም በእንስት ቍልፍ አገጣጥመው አምስቱንም ብስጥ ፈርጅና ስድስቱን ፈርጅ ብስጥም በተባት ቍልፍና በእንስት ቍልፍ አንድ አድርገው ሁሉም በቀለበት አንድ ይሁኑ ።

፲፪ ወታነብር ዘይፈደፍድ እምሠቅ ዲበ ደብተራ ዘተርፈ ወትከድን ከዋላ ደብተራ ።

ከብስጥ የተረፈውን ከአራት ኀብር የበለጠውን በአራት ኀብር ላይ አልብሰው ስታለብስም በፊት በኋላ አልብሰው ።

፲፫ እመተ ዘይተርፍ ሠቃተ ደብተራ እምገዳሚሃ ለደብተራ እምለፌ ወእምለፌ ይክድኖ ።

የምታለብሰው ከክበሮ ቤት እስከ ደጃፉ ከግራ እስከ ቀኝ ያለውን ዓምድ ከድንኳኑ ብስጥ የተረፈው ክንድ ሙሉ ይሸፍነው ። ዘፀ፡ ፴፮ ፲፱፡ ዘኍ፡ ፳፬ ፳ ።

፲፬ ወእግብር ማእሰ በግዕ ሕሡየ ዘሥርየቱ ኀብረ ያክንት ዘይከድኖ ለሠቅ ።

ብስጡንም ከላይ ጀምሮ እስከ ታች ድረስ የሚሸፍነው ተለፍቶ ቀለም የገባ የበግ ማእሰ መጸጺትን ሥራ ።

፲፭ ወእግብር አዕማደ ለደብተራ እምዕፀ ዘኢይነቅዝ ፡ ዘዐሥሩ በእመት ቆሙ ለአሐዱ ዓምድ ፡ ወራኅቡ እመት ወመንፈቀ እመት ።

ሸምሸር ሰጢን ከሚባል ከማይነቅዝ ዕንጨት ለድንኳኑ ዓምዶችን ሥራለት ፡ ይኸውም የአንዱ ዓምድ ቍመቱ ሃያ ክንድ ፡ ወርዱ ክንድ ከስንዝር ይሁን ።

፲፮ ወመሰምክተ ሥረዊሁ ክልኤቱ ለአሐዱ ዓምድ እንዘ ይሰመክ ዓምድ ለዓምድ ፡ ከማሁ ግበር ለኵሉ ዓምደ ደብተራ ።

(ከመ ይሰመክ) ዓምድ ከዓምድ ጋር ተጠጋግቶ ይቆም ዘንድ አንድ ዓምድ የሚቆምበት ምዕማዱ ሁለት ይሁኑ ፡ ለያንዳንዱም የድንኳን ዓምድ እንዲህ አድርገህ ሥራለት ።

፲፯ ወእግብር ዕሥራ አዕማደ መንገለ አዜብ ።

ሃያውን አዕማድ በአዜብ በኩል እንዲቆሙ አድርገህ ሥራቸው ።

፲፰ ወግበር ሎሙ ምዕማደ ዘብሩር አርበዐ ለዕሥራ አዕማድ ክልኤቱ ምዕማዱ ፡ ለአሐዱ ዓምድ ለክልኤሆሙ ገጸቲሁ ።

ለሃያው ዓምዶች አርባ የብር ምዕማድ ሥራላቸው ፡ ለአንዱ ዓምድ በሁለት ጥፍሮቹ የሚቆምባቸው ሁለት ምዕማድ ይሁኑ ። ዘፀ፡ ፴፮ ፳፬ ።

፲፱ ወካልእ እምገጸ ሰሜን ዕሥራ አዕማደ ።

ሁለተኛ በሰሜን በኩል ሃያ አዕማድ ይቁሙ ።

፳ ወምዕማዶሙ ዘይዐውሩ አዕማደ አርበዐ ዘብሩር ለለ አሐዱ ዓምድ ክልኤቱ ምእማዱ እምክልኤሆሙ ገጸቲሁ ፡

አዕማዱን የሚሸከሙ አርባ የብር አዕማድ ይሁኑ ፡ እያንዳንዱም ዓምድ የሚቆምባቸው ምዕማዶች ሁለት ሁለት ናቸው ።

፳፩ ወእምድኅር እምገጸ ደብተራ መንገለ ባሕር ግበር ሰብዓተ አዕማደ ።

ለድንኳኑ በስተፊት በምዕራብ በኩል የሚቆሙ ስድስት ዓምዶችን ሥራ ።

፳፪ ወክልኤተ አዕማደ ግበር ዓዲ ለመዓዝነ ደብተራ እምድኅር ።

ዳግመኛ በስተኋላ ለድንኳኑ መዓዝን ማቅኛ የሚሆኑ ሁለት ዓምዶችን ሥራ ።

፳፫ ዕሩያነ ይኩኑ ወይድረጉ ፍጹመ እምታሕቱ እስከ ላዕሉ ፡ ወከማሁ ግበር ለክልኤሆሙ መዓዝን ።

ዓምዶቹም ትክክል ይሁኑ ፡ እነዚህም ከላይ ጀምሮ እስከ ታች ድረስ አንድ ይሁኑ ፡ እንዲሁም ለሁለቱ መዓዝኖች ማቅኛ መሰብሰቢያ ሁለት ሁለት ምዕማድ ሥራላቸው ።

፳፬ ወይኩኑ አዕማድ ሰመንተ ፡ ወምዕማዲሆሙ ዘብሩር ዐሠርቱ ወሰብዐቱ ።

ስምንት አዕማድ ይሁኑ ፡ ከብር የተሠሩ ምዕማዶቻቸውም አሥራ ስባት ይሁኑ ።

፳፭ ወለለአሐዱ ዓምድ ክልኤቱ ክልኤቱ ምዕማዱ እምክልኤሆሙ ገጸቲሁ ።

የያንዳንዱም ዓምድ ምዕማድ በሁለት ጥፍሩ የሚቆምበቸው ሁለት ሁለት ይሁን ።

፳፮ ወግበር መናሥግተ ለአዕማደ ደብተራ እምዕፀ ዘኢይነቅዝ ።

ለደብተራ አሪት ሽቾሽር ሰጢን ከሚባል ከማይነቀዝ ዕንጨት ማገሮችን ሥራላቸው ። ዘፀ፡ ፴፮ ፴፩ ።

፳፯ ሐምስቱ መናሥግት እምአሐዱ ገጽ፤ ወሐምስቱ መናሥግት ዘመንገለ ባሕር ።

አምስቱንም ማገሮች በአንድ ወገን በሰሜን አድርግ አምስቱንም ማገሮች በአንድ ወገን ማለት በምዕራብ በኩል አድርግ ።

፳፰ ወግበር ለመንሥግ ዘማእከል ይዕዱ በማእከለ አዕማድ እምጽንፍ ኀበ ጽንፍ ።

ለማገሩም ከዳር እስከ ዳር ድረስ በዓምዶቹ መከከል ውስጥ ለውስጥ እንዲያልፍ አድርግለት፤ (እንደ ሽማኔ መወርወሪያ) ።

፳፱ ወለለአዕማድኒ ወለመናሥግት ቅፍሎሙ ወርቀ ወግበር አውቃፋተ ዘወርቅ ዘይከውኑ አብያተ ለመናሥግት ።

ዓምዶቹንም ማገሮቹንም ወርቅ ለብጣቸው፤ ለማገር ቤቶች የሚሆኑ የወርቅ አያ በሮችንም ሥራ ።

፴ ወግበር ለደብተራ በአርአያ ዘአርአይኩከ በደብር ።

ደብተራይቱንም በደብረ ሲና እንዳሳየሁህ አምሳል አድርገህ ሥራ ።

፴፩ ወግበር ላቲ መንጦላዕተ ዘኅብረ ያክንት ወኅብረ ከብድ ወለይ ክዑብ ወቢሶስ ፍቱል ወግበር በግብረ ምእናም ኪሩቤነ ።

መጋረጃውንም ከሰማያዊ፤ ከሐምራዊ ዕጽፍ ሁኖ ከተሠራ ቀይ ሐርና ከተፈተለ ከጥሩ በፍታ አድርግ፤ ኪሩቤልንም በግብረ መርፌ ጠልፈህ ሥራ፤ (ኪሩቤልን አስመስለህ ሥራ)። ዘፀ፡ ፳፭ ፲፡ ግብ፡ ሐዋ፡ ፯ ፵፬ ።

፴፪ ወግበር አርባዕተ አዕማደ እምዕፀ ዘኢይነቅዝ ወቅፍሎሙ ወርቀ ወአርእስቲሆሙ ወርቅ ወግበር ሎሙ አርባዕተ ምዕማደ ዘብሩር ።

ሽምሽር ሰጢን ከሚባል ከማይነቀዝ ዕንጨት ቈርጠህ አራቱን አዕማድ ሥራ፤ ወርቅንም ለብጣቸው ክባሶቻቸውም ወርቅ ይሁን፤ አራት የብር አዕማድንም ሥራላቸው።

፴፫ ወአንብር መንጦላዕተ ዲበ አዕማድ ወአብእ ውስተ ውሣጢሁ ለመንጦላዕት ታቦተ ዘመርጡል፤ ወይፍልጥ መንጦላዕት ውሣጢተ ወቀሰፋየ ቤተ መቅደስ ።

መጋረጃውን በአዕማድ ላይ አድርገው፤ ሕጉ ሥርዓቱ የሚጸናበት ታቦቲቱንም ከመጋረጃው ውስጥ አግባት መጋረጃውም የቤተ መቅደስ አፍአውንና ውስጡን የሚለይ ይሁን ። ዘኍ፡ ፫ ፴፩፡ ኢያ፡ ፬ ፲፩ ።

፴፬ ወይሜውር መንጦላዕት ታቦተ ዘመርጡል በቅድስተ ቅዱሳን ።

መጋረጃውም በቅድስተ ቅዱሳን ሁኖ ሕጉ ሥርዓቱ የሚጸናበት ታቦቲቱን ይጋርዳት ።

፴፭ ወአንብር ለማእድ እምአፍአሁ ለመንጦላዕት መንገለ መስዕ ወለተቅዋም አንብራ አንጻረ ማእድ በገጸ ደብተራ መንገለ አዜብ ።

ገበታውን ማእዱን ከመጋረጃው ውጭ በመስዕ በኩል አኑረው መቅረዚንም በገበታው ፊት ለፊት በአዜብ በኩል አኑራት ። ዘፀ፡ ፵ ፳፪፡ ዕብ፡ ፱ ፪ ።

፴፮ ወግበር ቤተ መንጦላዕተ ዘይከድና ለኆኅተ ደብተራ እምያክንት ወኅብረ ከብድ ወለይ ክዑብ፤ ወቢሶስ ክዑብ በብዑድ ግብረት ።

ከሰማያዊና ከሐምራዊ ሐር፤ ከቀይና ከብጫ ሐር፤ በጥልፍ አሠራር የተሠራ የደብተራ ኦሪትን ደጃፍ የሚጋርዳት መጋረጃ ሥራላት ። ዘፀ፡ ፴፮ ፴፯ ።

፴፯ ወግበር ለመንጦላዕት ሐምስተ አዕማደ እምዕፀ ዘኢይነቅዝ ወቅፍሎሙ ወርቀ፤ ወአርእስቲሆሙኒ ወርቅ፤ ወግበር ሎሙ ሐምስተ አዕማደ ዘብርት ።

ለመጋረጃውም ከማይነቅዝ ዕንጨት ቈርጠህ አምስት ምሰሶዎች አድርገህ ወርቅ ለብጣቸው፤ ኵላቦቻቸውም (ክባሶቻቸውም) ወርቅ ይሁን አምስት የብርት ምዕማድንም ሥራላቸው ።

## ምዕራፍ ፳፯።

፩ ወአግብር ምሥዋዐ ዘመሥዋዕት እምዕፀ ዘኢይነቅዝ፤ ዘሐምስቱ በእመት ኑኁ፤ ወሐምስቱ በእመት ራኅቡ፤ ርቡዐ ለይኩን፤ ወሠልሰ በእመት ይኩን ቆሙ ።

ርዝመቱ አምስት ክንድ፤ ወርዱ አምስት ክንድ የሚሆን ከማይነቀዝ ዕንጨት መሥዋዕት የሚሠዋበትን መሠውያ ሥራ ይኸውም አራት ገጽ ሁኖ ምዕዙን ይሁን ቁመቱም ሦስት ክንድ ይሁን ። ሕዝ፡ ፵፫ ፲፫ ።

፪ ወግበር ሎቱ አቅርንተ ዲበ አርባዕቱ መዓዝኒሁ፤ ወእምኔሁ ይፃኡ አቅርንቲሁ ወቅፍሎ ብርተ ።

በአራት መዓዝኑም ላይ ቀንዶችን አውጣለት ቀንዶቹም ከሱ የማይለዩ ሥረወዕ ይሁኑ ከብርትም ለብጠው ።

፫ ወግበር ሎቱ ቀጸላ፤ ወግበር ንዋያተ ለምሥዋዕ፤ ምግኅሣተ ወጸሕራተ ወፍያላተ ወመኖስሰ ሥጋ፤ ወመሳውደ እሳት፤ ወኵሎ ግበር እምብርት ።

በዙርያውም ከንፈር አውጣለት ለመሠውያውም ዕቃዎችን ሥራለት፤ አመዱን የሚያፍሱበት የብርት እንቅብ ደም የሚቀበሉበት የብርት እንሥራ፤ ጣሳዎች ሦስት ሐሳን ያለው የሥጋ መውጊያ፤ እሳቱን የሚጭሩበት

መጫረያዎችን ይህን ሁሉ ዕቃ ከብርት (ከናስ) ሥራው ።

፬ ወእግብር መጥበስቶ ለምሥዋዕ ስቅሱቀ ከመ መሥገርተ ዓሣ ዘብርት ፡ ወእግብር ሎቱ ለመጥበስት አርባዕተ ኅልቀታተ ዘብርት ፡ ውስተ አርባዕቱ መዓዝኒሁ ።

የብርት የሚሆን የመሠውያውንም መጥበሻ እንደ ዓሣ መረብ የተበሳሳ አድርገህ ሥራው ፡ ለመጥበሻውም በአራት መዓዝኑ ከብርት የተሠራ አራት ቀለበት ሥራለት።

፭ ወአንብሮ ለመጥበስት በቤተ መሥዋዕት ታሕተ ፡ ወይኩን በመንፈቀ ቤተ መሥዋዕት ።

መጥበሻውንም ከመሠውያው ውስጥ በታች አድርገው እሱም ብመሠውያው ቤት ውስጥ እኩሌታ ይንጠልጠል።

፮ ወግበር አርባዕተ አውቃፋተ ዘብርት በአርባዕቱ መዓዝኒሁ ፡ ከመ ይኩኑ አብያተ ለመግውሪሁ ።

ለመሸከሚያዎቹ ማንሻ ቤት እንዲሆኑ በአራቱ መዓዝን ከብርት የሚሠሩ አራት አምባሮችን ሥራ ።

፯ ወግበር መግውርተ እምዕፅ ዘኢይነቅዝ ለቤተ ምሥዋዕ ፡ ወቅፍሎሙ ብርተ ።

ለምሥዋዑ መሸከሚያዎች ከማይነቅዝ ዕንጨት ቁር ጠህ መሸከሚያዎችን መሎጊያዎችን ሠርተህ ብርት ለብጠጣቸው ። ዘኍ ፡ ፬ ፲፬ ፡ ኢሳ ፶፪ ፲፩ ።

፰ ወአብእ መግውሪሁ ውስተ አውቃፋት ዘላዕለ ገበዋተ ምሥዋዕ ከመ ያንሥኡ በሙ ።

ምሥዋዑን ያነሡበቸው ዘንድ ከምሥዋዑ ጐኖች በላይ በሉ ቀለበቶች መሎጊያዎቹን አግባ ።

፱ ወፍሉገ ይኩን ሰሌዳሁ በከመ አርአይኩከ በደብር ከማሁ ግበር ።

በጐኑም ፈለግ (ፈሳሽ) አውጣለት ፡ በደብረ ሲና እንዳሳየሁህ እንዲሁ አድርግ ።

፲ ወግበር ላቲ ዓፀደ ለደብተራ መንገለ አዜብ እንተ የማን ወመንጦላዕቱ ለዓፀድ እምቢሶስ ዕፁፍ ወኑኁ ምእት በእመት እምአሐዱ ምስማክ ።

ምሥራቅ ቀኝዋ በሚሆን በአዜብ በኩል ለደብተራ ኦሪት የሸማ አጥር መጋረጃ ሥራላት ፡ የሸማውም አጥር ዕጽፍ ሁኖ ከተሠራ ከነጭና ከብጫ ሐር የተሠራ የተፈተለ ይሁን ፡ አቈልቋዩም በአንድ ወገን መቶ ክንድ ይሁን።

፲፩ ወአዕማዲሁ ዕሥራ ፡ ወምዕማዲሆሙ ዕሥራ ዘበርት ወኖፃዳቲሆሙ ወጥነፊሆሙ ለአዕማድ ዘብሩር ።

የብርት የሚሆኑ ምዕማዶች ሃያ ፡ አዕማዶቹም ሃያ ናቸው ፡ የምሰሶዎቹም ቀለበቶችና ዘንጎች የብር ናቸው ።

፲፪ ከመዝ ግበር ለምስማክ ዘመንገለ ሰሜን ወመንጦላዕቱ ምእት በእመት ኑኁ ፡ ወአዕማዲሁ ዕሥራ ዘብሩር ፡ ወምዕማዲሆሙ ዕሥራ ዘብርት ፡ ወኖፃዳቲሆሙ ፡ ወጥነፊሆሙ ለአዕማድ ዘብሩር ።

በአዜብ በኩል እንደ ሠራኸው ፡ በሰሜንም በኩል እንደዚያው የሸማ አጥር መጋረጃ ሥራለት ፡ የሸማውም አጥር አቈልቋዩ መቶ ክንድ ይሁን ፡ የብር የሆኑ ዓምዶቹም ሃያ ናቸው ።

፲፫ ወለራኅበ ዓፀድ ዘገጸ ባሕር መንጦላዕቱ ሐምሳ በእመት ፡ ወአዕማዲሁ ዐሠርቱ ወምዕማዲሆሙ ዓሠርቱ ።

በስተምዕራብ ያለ የሸማው አጥር ስፋት አምሳ ክንድ ነው ፡ አዕማዱም አሥር ናቸው ፡ ምዕማዶቻቸውም እግሮቻቸውም ዓሥር ናቸው ። ዘፀ ፴፱ ፯ ፡ ዘኍ ፯ ፲፫ ።

፲፬ ወዐሠርቱ ወሐምስቱ በእመት ኑኁ ለመንጦላዕት እምገጸ አሐዱ ምስማክ ፡ ወአዕማዲሁ ሠለስቱ ፡ ወምዕማዲሆሙ ሠለስቱ ።

በአንድ ወገን ያለው የመጋረጃው አቈልቋዩ አሥራ አምስት ክንድ ነው ፡ አዕማዱም ሦስት ናቸው ፡ ምዕማዶቻቸውም ሦስት ናቸው ።

፲፭ ወእምካልእ ምስማክ ዐሠርቱ ወሐምስቱ በእመት ኑኁ ለመንጦላዕት ፡ አዕማዲሁ ሠለስቱ ፡ ወምዕማዲሆሙ ሠለስቱ ።

በሁለተኛው ወገን ያለው የመጋረጃው አቈልቋዩ አሥራ አምስት ክንድ ነው ፡ አዕማዱና ምዕማዶቻቸውም ሦስት ሦስት ናቸው ።

፲፮ ወለአንቀጸ ዐፀድ መንጦላዕቱ ዕሥራ በእመት ኑኁ ዘያክንት ወኅብረ ክብድ ወለይ ክዑብ ወቢሶስ ክዑብ ፡ ወብዑድ ይኩን በግብረ መርፍእ ፡ አዕማዲሁ አርባዕቱ ፡ ወምዕማዲሆሙ አርባዕቱ ።

በስተ መግቢያው ያለው ከሰማያዊ ሐር ዕጽፍ ሁኖ የተሠራ የመጋረጃው አቈልቋዩ ሃያ ክንድ ሁኖ በልዩ ግብረ መርፌ የተሠራ ይሁን አዕማዱና ምዕማዶቻቸውም አራት አራት ናቸው ፡ ዘሌዋ ፡ ፳ ፳ ።

፲፯ ወኵሉ አዕማድ ዓፀድ ዘዓውዱ ይትቀፈሉ ብሩረ ፡ ወአርእስቲሆሙኒ ብሩር ፡ ወምዕማዲሆሙኒ ብርት ።

በዙርያው ያሉ የሸማው አጥር ምሰሶዎች ሁሉ ብር ይለበጡ ፡ ክበሶቻቸውም የብር ናቸው ፡ ምዕማዳቸውም ብርት ይሁን ።

፲፰ ወኑኁ ለዓፀድ ምእት በእመት ፡ ወራኅቡ ሐምሳ በእመት ፡ ወቆሙ ሐምሳ በእመት ፡ እምቢሶስ ክዑብ ፡ ወምዕማዲሆሙ ብርት ።

ዕጽፍ ሁኖ ከተፈተለ ከነጭና ከብጫ ሐር የተሠራው የሸማው አጥር (መጋረጃው) ወደላይ ቍመቱ አምሳ ክንድ ነው ፡ የአዕማዱም ምዕማድ የብርት ነው ።

፲፱ ወኵሉ ንዋየ ደብተራ በኵሉ ግብሩ ፡ ወመታግሪሁ ወመታክሊሁ ፡ ወመታክለ ዓፀዱ ብርት ።

የደብተራ ኦሪት ዕቃ ሁሉ በሚሠራበት ሥራ ሁሉ (መታግሪሁ) ቍልፉ (መታክል) ክስማው ብርት ይሁን ፡ የአደባበዩ ክስማውም የናስ ይሁኑ ።

፳ ወአንተ አዝዞሙ ለደቂቀ እስራኤል ይንሥኡ ቅብዐ

አንተም መብራቱን ያበሩ ዘንድ ለመብራት መጀመ

ዘይት ዘቀዳሚ ቅስመታ ንጹሐ ወውጉአ፡ ለብርሃን ከመ ያኅትዉ ማኅቶተ በውስተ ደብተራ እፍአ እመንጦላዕት ዘቅድመ ትእዛዝ ።

ፊያ የተቀዳውንና መላልሶ የተጠራውን ዘይቱን ያመጡ ዘንድ የእስራኤልን ልጆች አምጡ ብለህ እዘዛቸው፡ ይህም ትእዛዝ በሚጠበቅበት በአምሬቱ ክንድ አንጻር ከመ ጋረጃው ውጭ ይሁን ።

፳፩ ወየኃትዉ አሮን ወደቂቁ እምሠርክ እስከ ነግህ፡ ቅድመ እግዚአብሔር ሕግ ለዝሉፉ ለትውልዶሙ፡ እምደቂቀ እስራኤል ።

ይኸውንም ልጆቹና አሮን ከማታ ጀምሮ እስከ ጧት ድረስ በእግዚአብሔር ፊት ሲያበሩ ይኑሩ፡ ይኸውም ከእስራኤል ለሚወሰዱ ሰዎች ለዘለዓለሙ ሥርዓት ይሁን ። ዘሌዋ፡ ፳፬ ፪ ።

ምዕራፍ ፳፰ ።

ምዕራፍ ፳፰ ።

፩ ወአቅርብ ኀቤከ ለአሮን እኁከ ወለደቂቁ ምስሌሁ እም ደቂቀ እስራኤል ከመ ይሡዑ ሊተ አሮን ወናዳብ ወአብዩድ ወአልአዛር ወይታምር ።

ከእስራኤል ልጆች ለይተህ ወንድምህ አሮንን ከልጆቹ ጋር ወደ አንተ አቅርበው አሮንና ልጆቹ አብዩድ ናዳብ አልአዛርና ይታምር ይሠውልኝ ዘንድ ።

፪ ወግበር አራዘ ቅዱሰ ለአሮን ለክብር ወለሡራኄ ።

ለክብር ለጌጽ እንዲሆን ለወንድምህ ለአሮን የከበረ ልብስ ቀሚስ አሠራለት ። ዘኁ፡ ፳ ፳፮

፫ ወአንተ አይድዕ ለኵሉ ጠቢባነ ልብ ዘመላእኩ ላዕሌሆሙ መንፈሰ ጥበብ ወእሙንቱ ይግበሩ አራዘ ቅዱሰ ለቤተ መቅደስ፡ በዘቦቱ ይቄድሱ ኪያየ ።

የጥበብን ሀብት ላሳደርኩባቸው ዕውቀት ላላቸው ሁሉ አንተ ንገር፡ እነሱም (ካህናቱ) ለቤተ መቅደስ መገልገያ ሊሆን እኔን የሚያመሰግኑበትን የተለየ ልብስ ይሥሩ።

፬ ወእሉ አልባስ ዘይገብሩ ኤፉድ ወሎግዮ፡ ወጽዱሬ ወቢሦስ ዘቀኖጽሮ ወአክሊል ወድርማንቅ ዘሐቂ ወቅናታት፤

የሚሠሩባቸውም ልብሶች እሊህ ናቸው፡ (ኤፉድ) ልብሰ መትከፍ (ሎግዮ) የደረት ልብስ (ጽዱሬ) እጅ ሰፊ ቀሚስ፡ (ወቢሦስ ዘቀኖጽሮ) ከነጭ ሐር የተሠራ እጀጠባብ አክሊል ኩፌት ወገባቸውን የሚታጠቁበት ልባልብ ዝናር።

፭ ወእሙንቱ ይንሥኡ ወርቀ ወያክንተ ወኅብረ ከብድ፡ ወለየ ክዑበ ወቢሦሰ ።

እነሱም ወርቁን ሰማያዊውን ሐር ዕጽፍ ሁኖ የተሠራ የተፈተለ ቀይ ሐር ብጫ ሐር (ከእስራኤል ይውሰዱ)።

፮ ወይግበሩ ኤፉደ እምወርቅ፡ ወያክንት ወኅብረ ከብድ ወለይ ወቢሦስ ፍቱል በግብረ መርፍእ፡ ወግብሩ ግብረ ምእናም ብዑድ ።

ከወርቅ ከሰማያዊ ሐር፡ ከብጫ ሐር፡ ከሐምራዊ ሐር ዕጽፍ ሁኖ ከተሠራ ቀይ ሐር ከተፈተለ ከነጭ ሐር ከዚህ ከራቱ ኅብር ግምጃ ጋር ወርቁን በጥልፍ እያስማሙ የጫንቃውን ልብስ በግብረ መርፌ ሥራ ይሥሩ፡ የዚህም ሁሉ ሥራው በተለየ በግብረ መርፌ ሥራ ይሁን ።

፯ ወክልኤተ ይኩና መታክፊሁ እለ ይትላጸቃ በበይናን አሐቲ ዲበ አሐቲ እምክልኤሆን ገጸ ግብረቶን ።

በጫንቃው የሚለብሳቸው የኤፉድ ፊርጆች አሠራራቸው ሁለት ወገን ሁኖ አንዲቱ ከአንዲቱ ጋር እርስ በርሳቸው የተጋጠሙ ሁለት ይሁኑ ። ዘፀ፡ ፴፱ ፬ ።

፰ ወእንመተ ትብልያሁ ዘላዕሌሁ እምግብረቶን ድሙራተ ይኩና ዘወርቅ ወያክንት፡ ወኅብረ ከብድ ወለይ ክዑብ፡ ወቢሦስ ክዑብ ።

ሥራቸውም ከወርቅ ከሰማያዊ ሐር ከሐምራዊ ሐር፡ ዕጽፍ ሁኖ ከተሠራ ብጫ ሐር፡ ዕጽፍ ሁኖ ከተፈተለ ቀይ ሐር የሚሆን (በአሮን) ጫንቃ ላይ ያሉ የኤፉድ ሥራዎች በጫንቃው ላይ የተገናኙ ይሁኑ ።

፱ ወንሣእ ክልኤተ አእባነ መረግድ ወግልፍ ላዕሌሆሙ አስማተ ደቂቀ እስራኤል ።

የመረግድ አዕናቍ አምጥተህ የአሥራ ሁለቱ ነገደ እስራኤል ስም በላያቸው ላይ ቅረጽበት ።

፲ ስድስተ አስማተ ላዕለ አሐዱ እብን፡ ወስድስተ አስማተ ላዕለ አሐዱ እብን በበአዝማዲሆሙ ።

ስድስቱን ስሞች በአንድ ዕንቊ፡ ስድስቱን ስሞች በአንድ ዕንቊ፡ በየወገናቸው ቅረጽ ።

፲፩ ወግበር ግብረ ዘኪን ኀርወተ ዓይነ ማኅተም፡ ወበክልኤቱ አእባን ዘላዕሌሆሙ አስማተ ደቂቀ እስራኤል ።

የእስራኤልን ልጆች አስማት በተጻፈባቸው በሁለቱ አዕናቍ ዙርያ ዕንቊን የሚይዝ የወርቅ ቀለበት አበጅለት በዕንቊ ላይ የሚጻፈውም የስማቸውን አቀራረጽ እንደ ማኅተም አቀራረጽ አድርገህ በጥበብ ሥራ ።

፲፪ መአኅዘ ወርቅ ትገብር በዓውዶሙ ወታነብሮሙ ለክልኤቱ አእባን ላዕለ መትከፈ ኤፉድ፡ ተዝካረ በእንቲአሆሙ ።

ሁለቱንም ዕንቆች ለእስራኤል መታሰቢያ ሊሆኑ በልብሰ መትከፍ በኤፉድ ላይ በሐር ጠልፈህ አያይዛቸው ።

፲፫ ወይነሥእ አሮን አስማቲሆሙ በቅድመ እግዚአብሔር ላዕለ ክልኤቱ መታክፍቲሁ ለአዘክሮቶሙ፡ ወግበር አራዊተ ምድር እምወርቅ ንጹሕ ።

አሮንም የአሥራ ሁለቱ ነገደ እስራኤል ስም የተጻፈባቸው አዕናቍ ያሉበትን ኤፉድን እስራኤልን በእግዚአብሔር ፊት ለማሳሰብ በሁለት ጫንቃዎቹ ላይ ለብሶ ይግባ ።

፲፬ ወአግብር ክልኤተ ሰናስለ እምወርቅ ንጹሕ ድሙረ ፡ ግብረ ጽፉረ ወአንብር ሰናስለ ዲበ አራዊተ ምድር ።

ለሁለቱም እበቦች እንደ ቋድ ሥራ የተታታ አድርገህ ከጸሩ ወርቅ ሁለት የወርቅ ሰንሰሎችን አሠራ፡ ሁለቱንም የወርቅ ሰንሰለቶች በሁለቱ የወርቅ እበቦች ላይ አኑር ።

፲፭ ወግበር ሎግዮ ዘፍትሕ በግብረ ምእናም ፡ በሐሳበ ኤፉድ ግበር በወርቅ ወበያክንት ወበኅብረ ከበድ ወለይ ክዑብ ወቢሦስ ክዑብ ።

ከዚህም በኋላ ኢታምልክ የሚጠበቅበት በግብረ መርፌ ሥራ የተሠራ ልብሰ እንግድዓ ሥራ ፡ ወርዱንም ቁመቱንም በኤፉድ ልክ አድርገህ ከአራቱ ኅብር አምስተኛ ወርቅ ሥራው ። ዘሌዋ፡ ፰ ፰፡ ኢሳ፡ ፶፱ ፲፯ ።

፲፮ ወትገብሮ ርቡዐ ወውጡሐ ወይኩን ዓጽፍ ዘእመት ኑኁ ፡ ወእመት ራኅቡ ።

ይህንም በአራት ወገን ምዕዙን አድርገህ የተነፋ አድርገው ልብሰንቱም አቈልቋዩ ክንድ ወርዱም ክንድ ይሁን።

፲፯ ወአንብር ላዕሌሁ አእባነ በአርባዕቱ ያታ ፡ አሐዱ ያታ ዘእብን ይትገበር ዘሰርድዮን ወዘጳዝዮን ወዘመረግድ ።

እነዚህንም ዕንቆች በሎግዮ ላይ በአራት ወገን አኑራቸው ፡ ከዕንቊ የተሠራ አንድ ወገን ሰርድዮን ፡ ጳዝዮን መረግድ ከሚባል ዕንቊ ነው ።

፲፰ ወክልእ ያታ ዘእብን ከመ ፍሕም ወሰንፔር ወኢያሰጲድ ።

የሁለተኛውም ወገን የዕንቊ ስም ፍሕም ፡ ሰንፔር ፡ ኢያሰጲድ የሚባል ሦስት ዕንቊ ነው ።

፲፱ ወሣልስ ያታ ዘለግርዮን ወአከጥስ ፡ ወአሜቴስጢኖስ ።

ሦስተኛውም ወገን ለግርዮን አካጥስ አሜቴስጢኖስ የሚባል ሦስት ዕንቊ ነው ።

፳ ወራብዕ ያታ በእብን ዘኅብረ ወርቅ ወቢረሌ ፡ ወሦም ወይኩን ልቡጠ በወርቅ ፡ ወእሱረ በወርቅ በበያታሁ ።

በዕንቊ የተሠራ አራተኛውም ወገን ኅብረ ወርቅ ቢረሌ ሦም የሚባል ሦስት ዕንቊ ነው ፡ ይኸውም በየወገን በየወገኑ በወርቅ የተለበጠ በወርቅ የታሰረ ይሁን ።

፳፩ ወእእባኒሁ ይትገበሩ በአስማቲሆሙ ለዐሠርቱ ወክልኤቱ ሕዝበ እስራኤል ፡ ወይትገለፉ ከመ ግልፈተ ዓይነ ማኅተም ለለስሞሙ ለዐሠርቱ ወክልኤቱ ሕዝበ እስራኤል !

ዕንቆቹም በአሥራ ሁለት የእስራኤል ልጆች ስሞች ይሠሩ እንደ ማኅተም መልክ አቀራረጽ ሁነው ለአሥራ ሁለቱ ነገደ እስራኤል በየስማቸው ይቀረጹ ።

፳፪ ወግበር ሰናስለ ለሎግዮ ዘጽፍሮ ወጽፍርሁ ከመ ዘርዚቅ ዘወርቅ ንጹሕ ።

ለተጐነጐነው ሎግዮም የወርቅ ሰንሰለት ሥራለት ፡ ከጸሩ ወርቅ የተሠራው ሰንሰለትም (ከመ ዘርዚቅ) እንደ ዓሣ መረብ የተበሳሰ ይሁን ።

፳፫ ወግበር ክልኤተ ኅልቀታተ ወርቅ ፡ ወታነብሮሙ ለክልኤቱ ኅልቀታት ላዕለ ክልኤቱ ጽነፊሁ ለሎግዮ ።

ሁለት የወርቅ ቀለበቶችን ሠርተህ ሁለቱንም ቀለበቶች በሁለቱ የሎግዮ ዘርፍ ላይ አኑራቸው ።

፳፬ ወታነብሮሙ ለክልኤቱ ጽፍሮ ወርቅ ላዕለ ክልኤቱ ኅልቀታት ዘጽንፈ ሎግዮ ።

እንደ ዓሣ መረብ የተበሳሱ ሁለቱን የወርቅ ሰንሰለቶችንም በሎግዮ ዳርቻ ላይ ባሉ በሁለቱ የወርቅ ቀለበቶች ላይ በሁለት ወገን አኑራቸው ።

፳፭ ወለክልኤቱ ጽነፊሁ ታነብር ክልኤተ ጽፍሮ ላዕለ ክልኤቱ ክበበ ጥውዮ ፡ ወታነብሮ ላዕለ መትከፈ ኤፉድ መንገለ ገጹ በማኅበርቱ ።

ሁለቱን የወርቅ ሰንሰለቶች በኤፉዱ ጫንቃ ላይ በስተፊቱ በሁለት ወገን አገናኛቸው ።

፳፮ ወግበር ክልኤተ ሕልቀታተ ወርቅ ፡ ወታነብሮሙ ላዕለ ክልኤቱ ጽነፊሁ ለሎግዮ ኀበ ከንፈሩ ፡ ኀበ ዘየኃልፍ ኤፉድ እንተ ውስጥ ።

ለእነዚህ ሁለት የወርቅ ቀለበቶች ሥራላቸው ፡ እነዚህም ሁለት የወርቅ ቀለበቶች ኤፉድ በውስጡ በሚያልፍበት በከንፈረ ሎግዮ ላይ በሁለት ወገን አኑራቸው ።

፳፯ ወግበር ክልኤተ ኅልቀታተ ወርቅ ወታነብሮሙ ላዕለ ክልኤቱ መታክፈ ኤፉድ ኀበ ይትረአይ መንገለ ገጹ በማኅበርቱ ፡ መልዕልቴሁ ለእንመተ ኤፉድ ።

ዳግመኛ ለኤፉድና ለሎግዮ ሁለት የወርቅ ቀለበቶች ሥራላቸው እነዚህንም ሁለት የወርቅ ቀለበቶች በኤፉድ ሥራ ላይ ኤፉድና ሎግዮ በሚገናኙበት ፊቱም በሚተያይበት በሁለቱ የኤፉድ ጫንቃዎች ላይ አኑራቸው ።

፳፰ ወያስተአኀዝዎ ለሎግዮ እምኅልቀታቲሁ ኀበ ኅልቀታተ ኤፉድ በፈትለ ያክንት ፡ ከመ ይኩን ላዕለ እንመተ ኤፉድ ወኢያንጠልል ሎግዮ እምኤፉድ ።

ሎግዮ በኤፉድ ሥራ ላይ ይሆን ዘንድ ሎግዮም ከኤፉድ ተለይቶ እንዳይነጣጠል ፡ ሎግዮን ከቀለበቶቹ ወደ ኤፉድ ቀለበቶች በሰማያዊ ሐር ፈትል ያያይዙት ።

፳፱ ወይንሣእ አሮን አስማተ ደቂቀ እስራኤል መልዕልተ እንግድዓሁ ለሎግዮ ዘፍትሕ ፡ በበዊአቱ ውስተ መቅደስ ከመ ያዘክሮሙ ቅድመ እግዚአብሔር ዘልፈ ።

እስራኤልን ዘወትር በእግዚአብሔር ፊት በበጎ ነገር ሊያሳስባቸው አሮን ወደ ቤተ መቅደስ በሚገባበት ጊዜ (የቸርነቱ ፍርድ በሚፈረድበት) በሎግዮ በደረቱ ላይ አድርጎ የእስራኤልን ልጆች ስም ይዞ ይሂድ ።

፴ ወታነብር ኀበ ሎግዮ ዘፍትሕ ፡ መብርሂያተ ወማኅተማተ ወይኩኑ ላዕለ ልበ አሮን ሶበ ይበውእ ቤተ መቅደስ

የቸርነቱ ፍርድ በሚፈረድበት ፡ በሎግዮ በሐርና በወርቅ ማርዳ የተቈለፉ ንሥራ ሁለቱን አዕናቊ በሎግዮ ላይ

ቅድመ እግዚአብሔር ያብእ ፍትሐሙ ለውሉደ እስራኤል ዲበ እንግድዓሁ ዘልፈ ።

፴፫ ወግበር ጽጌሬ ዘሥለንታሁ በያክንት ።

፴፬ ወአፈ መልበስቱ እምኔሁ ይኩን ማእከለ በዓውዱ በግብረ ምእናም፤ ወድማሬሁ እንም እምኔሁ ከመ ኢይትበተክ ።

፴፭ ወግበር እመልዕልቴሁ በዓውዱ መትሕተ መልበስቱ ከመ ፍሬያተ ሮማን ዘያክንት ወኅብረ ከብድ ወለይ ክዑብ ወቢሦስ ክዑብ ።

፴፮ ወጸናጽላተ ወርቅ በማእከለ ሮማን፤ ወሮማን ማእከለ ጸናጽለ ወርቅ መልዕልተ ጽጌሬ እንተ ዓውድ፤ ወይከውን ላዕለ አሮን ሰተልእክ ።

፴፯ ወይግበር አሮን ሶበ ይሠውዕ በቃል ዘይሰማዕ እንዘ ይበውእ ቤተ መቅደስ ቅድመ እግዚአብሔር፤ ወእንዘኂ ይወጽእ ከማሁ ከመ ኢይሙት ።

፴፰ ወግበር ቈጽለ ወርቅ ረቃቀ እምወርቅ ንጹሕ ወትገ ብር ላዕሌሃ አርአያ ማኅተም ቅዱስ ለእግዚአብሔር ።

፴፱ ወታነብራ ዲበ ዘኅብረ ያክንት ፍትሎ ወታነብራ ዲበ አክሊል መንገለ ፍጽሙ፤ ወትኩን ውስተ ፍጽሙ ለአሮን ።

፵ ወይንሣእ አሮን ኃጢአተ ቅድሳት ዘቀደሱ ውሉደ እስራኤል እምኵሉ ሀብተ ቅድሳቶሙ፤ ወይኩን ውስተ ፍጽሙ ለአሮን ከመ ይኩን ሎሙ ሥምረ ለእግዚአብሔር ።

፵፩ ወትገብር አራዘ እምቢሦስ፤ ወአክሊለ ዘቢሦስ፤ ወቅ ናተ ዘኅብረ ግብረቱ ።

፵፪ ወለደቂቀ አሮን ትገብር ሎሙ አልባሰ ዘቢሦስ፤ ወቅ ናታተ ወቆብዓተ ወይኩን ለክብር ወለእንክሮ ።

፵፫ ወአግብር ሎሙ ድርማንቀ ዘአጌ ከመ ይሠውሮሙ ኀፍረቶሙ ፤ ወንበ ይከድና እምሐቌ እስከ መናቅዕ ለይኩና ።

፵፬ ወታለብሶ ለአሮን እኁከ ወለደቂቁኒ ምስሌሁ፤ ወቅብ ኦሙ ወአጽሕዶሙ እደዊሆሙ ወእገሪሆሙ፤ ወቀድሶሙ ከመ ይሡኡ ሊተ ።

፵፭ ወከማሁ ለይልበሱ አሮን ወደቂቁ ሶበ ይበውኡ ው ስተ ደብተራ ዘመርጡል ሶበ ይቀርቡ ይሡዑ ኀበ ምሥ ዋዐ ቤተ መቅደስ ።

፵፮ ወኢያምጽኡ ላዕሌሆሙ ኃጢአተ ወኢይሙቱ፤ ሕግ ዘለዓለም ውእቱ ሎቱ ወለዘርኡ እምድኅሬሁ ።

አኑራቸው፤ እነዚህም አሮን ስለ እስራኤል ልጆች ሊያስ ፈርድላቸው ልመናቸውን ይዞ ወደ ቤተ መቅደስ በሚገባ በት ጊዜ በደረቱ ላይ እንደ ወርቅ ማርዳ ይሁኑ ።

ለነዚህም ከእግር እስከ ራሱ ከሰማያዊ ሐር የተሠራ እጀ ሰፊ ቀሚስ ሥራለት ። ዕብ፥ ፱ ፳፫ ።

አንገትጌውም በግብረ መርፌ የተጠለፈ ሁኖ በዙር ያው መካከል ሥረ-ወዕ ይሁን፤ እንዳይቀደድም እንደ ጥሩር የተሠራ ጥልፍ በአንገትጌው ዙርያ ይሁንበት ።

በታችኛውም ዘርፍ ዙርያ ከሰማያዊ ከሐምራዊ ከቀ ይም ግምጃ እንደ ሮማን ፍሬ ያለ ሥራለት፤ የወርቅ ጸና ጽሎችንም ሥራለት ።

በሞሉጣ ግምጃ ላይ በዙርያው ጸናጽል መካከል የወ ርቅ ሮማንን በወርቅ ሮማን መካከል የወርቅ ጸናጽልን አድ ርግበት፤ ይህም ሁሉ በአሮን ላይ ሁኖ ለመገልገያ ይሁን።

አሮንም ወደ ቤተ መቅደስ ሲገባ በእግዚአብሔር ፊት በሚሠዋበት ጊዜ በሚሰማ ቃል ያድርግ፤ ሲወጣም (እን ዳይቀሠፍ) እንዲሁ ያድርግ ።

ወርቁን ከጸሩ ወርቅ ለይተህ እንደ ቅጠል አሳስተህ ሥራ፤ በላይዋም ላይ እንደ ማኅተም ቅርጽ (ራስ ወርቅ) ቅረጽበት፤ በራስ ወርቁም ላይ (አህያ ሽራህያ አልሻዳይ) የሚባሉ ቃላት ቅረጽበት ።

ይህችንም እንደ ራስ ወርቅ ያለችውን ከሰማያዊ ኅብ ር በተፈተለ ክር በአሮን አክሊል ላይ በስተፊቱ አን ጠልጥላት ። ፩ ዜና መዋ፥ ፲፯ ፳፱፤ ዘካ፥ ፲፬ ፳ ።

በአሮንም ግምባር ላይ ትሁን፤ እስራኤል ስለ ኃጢአ ታቸው ከከብታቸው ለይተው ካቀረቡት ሁሉ ጋር ለኃጢ አታችን ማስተሥረያ ይሆነናል፤ እግዚአብሔር ይቀበለ ናል ብለው አክብረው ያቀረቡት ይህን ራስ ወርቅ አሮን በራሱ ላይ ደፍቶ ወደ ቤተ መቅደስ ይግባ ።

ከነጭ ሐር፤ እጀ ጠባብ ቀሚስ ከነጭ ሐርም ኵፌት ከአራቱ ኅብር የተጠለፈ ዝናርንም ሥራ ።

ለአሮንም ልጆች ሊከበሩበት ሊደነቁበት ከነጭ ሐር ቀሚስ ዝናር ኵፌት ሥራላቸው ።

ኃፍረታቸውን እንዲሠውርላቸው ከወገባቸው እስከ ቁርጭምጭማቸው የሚያለብሳቸው የነጭ ሐር ልብልብ አሠራላቸው ። ዘፀ፥ ፴፬ ፳፯፤ ሕዝ፥ ፵፬ ፲፯ ።

(ይህንም) ልብስ (አስቀድመህ) ለወንድምህ ለአሮን አልብሰው፤ ከሱም ጋራ ለልጆቹ አልብሳቸው (ሃብተ ክህ ነት የሚቀበሉበት) አራት ሽቱ አምስተኛ ዘይትንም ቀብ ቸው፤ በሽቱና በዘይትም እግሮቻቸውንና እጆቻቸውን አለዝበህ ለኔ መሥዋዕት እንዲያቀርቡልኝ አክብረህ ሹማቸው ። ዘፀ፥ ፳ ፯፤ ሌዋ፥ ፲ ፯ ።

አሮንና ልጆቹ ወደ ደብተራ ኦሪት በገቡ ጊዜ በምስ ጋና ማደሪያው በቤተ መቅደስ አጠገብ ወዳለ መሠውያም ሊሠዉ በቀረቡ ጊዜ እንዳዘዝኩት ያለ ልብስ ይልበሱ ።

በራሳቸውም ዕዳ በደል እንዳያመጡና እንዳይቀሠፉ ለሱና ለልጆቹ፤ ከሱም በኋላ ለልጅ ልጆቹ ለዘለዓለሙ ሥርዓት ነው፤ (ይሁን)። ዘሌዋ፥ ፳ ፲፱ ።

| ምዕራፍ ፳፱ ። | | ምዕራፍ ፳፱ ። |
|---|---|---|
| ወዝ ውእቱ ዘትገብር ሎሙ አመ ትቄድሶሙ ከመ ይትለአኩኒ ንሣእ አሐደ ላሕመ እምአልሕምት ወአባግዐ ንጹሐነ ክልኤተ ። | ፩ | እንዲያገለግሉኝ አክብረህ በሾምኻቸው ጊዜ የምታደርግላቸው ሥራ ይህ ነው ፤ (ለነሱ የምትሠዋላቸው) አንድ ወይፈንና ሁለት ንጹሐን በጎችን አምጣ አለው ። |
| ወኅብስተ ናእት ልዉሰ በቅብዕ ወጸራይቀ ናእት ዘበ ቅብዕ ዘሥንዳሌ እምሥርናይ ትገብሮን ። | ፪ | በዘይት የታሸ የቂጣ እንጀራና በዘይት የታበቀ የሥንዴ ድፎን ልጦ ጐርዶ ከወጣለት ሥንዴ ሥራላቸው ። |
| ወታነብሮን ዲበ መሶብ ወታቄርቦን በመሶብ ወለላሕም ወለክልኤቱ አባግዕ ። | ፫ | ሁለቱን በጎችና ወይፈኑንም በመሶብ አድርገህ (ለመሥዋዕት) አቅርባቸው ። |
| ወለአሮን ወለደቂቁ ታቀርቦሙ ኀበ ኆኀተ ደብተራ ዘመርጡል ፤ ወታሐጽቦሙ በማይ ። | ፬ | አሮንና ልጆቹንም በውኃ አጥበህ ወደ ደብተራ ኦሪት አቅርባቸው ። ዘሌዋ፡ ፴ ፲፪ ፤ ዕብ፡ ፲ ፳፪ ። |
| ወነሢአከ አልባሲሁ አልብሶ ለአሮን እኁከ ፤ ልብሰ ቢሦስ ወጸዳሬ ወኤፉደ ወሎግዮ ፤ ወታጸንዖ በሰናስሊሃ ። | ፭ | ልብሶቹንም አምጥተህ ወንድምህ አሮንን አልብሰው የምታለብሰውም ልብስ የነጭ ሐር ቀሚስ ሞሉጣ ግምጃ ኤፉድንና ሉግዮን ነው ፤ እነዚህንም (በክበበ ጥውዮ) ሰንሰለት አሥራቸው ። ዘሌዋ፡ ፰ ፯ ። |
| ወታነብር አክሊለ ዲበ ርእሱ ፤ ወታነብር ቀጸላ ዘወርቅ ዲበ አክሊሉ ። | ፮ | ኩፌቱን በራሱ ላይ ድፋለት ፤ በኩፌቱም ላይ የራስ ወርቅ አድርግለት ። ዘኁ፡ ፴፫ ፳፰ ። |
| ወትነሥእ እምቅብዕ ዘበረከ ወትክዑ ዲበ ርእሱ ወትቀብዖ ። | ፯ | ከበረከኸውም ዘይት አምጥተህ በራሱ ላይ አፍስስበት (ከእግር እስከ ራሱ አካሉን) ቅባው ። |
| ወለደቂቁኒ ታቀርቦሙ ወታለብሶሙ አልባሲሆሙ ፤ ወታቀንቶሙ ቅናታቲሆሙ ። | ፰ | ልጆቹንም አቅርበህ የሚገባ ልብሳቸውን አልብሳቸው የወርቅ ዝናራቸውንም አስታጥቃቸው ። |
| ወትወዲ ዲቤሆሙ ቅብዐ ወይከውኑኒ ሠዋዕተ ሊተ ለዓለም ወትፌጽም እዴሁ ለአሮን ወእደወ ደቂቁ ። | ፱ | ኩፌትንም በራሳቸው ድፋባቸው ፤ መሥዋዕት የሚሠዉ ለዘለዓለሙ ለኔ አገልጋዮች ይሆኑኛል ፤ የአሮንንም ቀኝ እጁን የልጆቹንም ቀኝ እጃቸውን ቅባ ። |
| ወታቀርብ ላሕመ ኀበ ኆኀተ ደብተራ ዘመርጡል ወያ ነብሩ አሮን ወደቂቁ እደዊሆሙ ዲበ ርእሰ ላሕም ለቅ ድመ እግዚአብሔር ፡ በኀበ ኆኀተ ደብተራ ዘመርጡል ። | ፲ | ወይፈኑን ወደ ደብተራ ኦሪት በር አቅርበው አሮንና ልጆቹም በቤተ እግዚአብሔር ፊት ለፊት ቁመው እጃቸውን በወይፈኑ ራስ ላይ ይጫኑ ። ዘሌ፡ ፳ ፲፬ ። |
| ወተሐርዶ ለላሕም በቅድመ እግዚአብሔር ኀበ ኆኀተ ደብተራ ዘመርጡል ። | ፲፩ | ላሙንም በደብተራ ኦሪት ደጃፍ በእግዚአብሔር ፊት አረደው አወራርደው ። |
| ወትነሥእ እምደመ ላሕም ወትወዲ ዲበ አቅርንተ ምሥዋዕ ዘቤተ መቅደስ በአጽባዕትከ ወዘተርፈ ኵሉ ደሞ ትክዑ ጥቃ ቤተ መቅደስ ። | ፲፪ | ከላሙም ደም ከፍለህ በጣትህ እየጠለቅህ በቤተ መቅደስ አጠገብ ባለ በአቅርንተ ምሥዋዑ ላይ አድርገው የተረፈውን ደሙ ግን በቤተ መቅደስ አጠገብ ባለ በምሥዋዑ ዙርያ አፍስሰው ። ዘፀ፡ ፴ ፪ ። |
| ወትነሥእ ኵሎ ስብሐ ከርሡ ፤ ወከብዶ እንተ ትንእስ ወክልኤተ ኵልያቶ ፡ ወስብሐ ዘላዕሌሆን ወታነብር ውስተ ምሥዋዕ ። | ፲፫ | የሆድ ዕቃውን ጮልገል ጉበቱን ግራ ቀኝ ኵላሊቱን በነዚህ ላይ ያለውን ስብ ሁሉ አምጥተህ በምሥዋዑ ላይ አኑረው ። ዘሌዋ፡ ፫ ፫ ። |
| ወሥጋ ላሕም ወማእሰ ወጸፍዖ ታውዒ በእሳት ፤ አውጺአከ አፍአ እምትዕይንት ፤ እስመ ዘኃጢአት ውእቱ ። | ፲፬ | የላሙን ሥጋና ቁርበቱን ፈርሱን ግን አፍአ አውጥተህ በእሳት አቃጥለው የኃጢአት ነውና ። |
| ወትነሥእ አሐደ በግዐ ወያነብሩ አሮን ወደቂቁ እደዊሆሙ ላዕለ ርእሰ በግዕ ። | ፲፭ | ከሁለቱ በጎች አንዱን በግ አምጥተህ አሮንና ልጆቹ በበጉ ራስ ላይ እጃቸውን ይጫኑበት ። |
| ወተሐርዶ ለውእቱ በግዕ ፤ ወትነሥእ ደሞ ወትክዑ ላዕለ ምሥዋዕ ፤ ወውስተ ኵሉ ዓውዱ ትነስንስ ። | ፲፮ | ያንንም በግ አርደህ አወራርደህ ደሙን አምጥተህ በምሥዋዑ ላይ አፍስሰው ፤ (የተረፈውንም) በመሠውያ ዙርያ ረብርበው ። |
| ወትጠብሖ በበመሌሊቱ ወተሐፅብ ንዋየ ውስጡ ወእገሪሁ ወታነብር ኀበ ዘሌለይከ ። | ፲፯ | በየስልት በየስልቱ አርደህ አወራርደህ ሆድ ዕቃውንና እግሩን አጥበህ (የበጉን ሥጋ) ለይተህ ለይተህ በኖር ክበት ላይ አኑረው ። ዘፍ፡ ፰ ፳፩ ። |
| ወታንርግ ኵሎ በግዖ ላዕለ ምሥዋዕ ፤ ቍርባን ውእቱ ለእግዚአብሔር ። | ፲፰ | በጉንም በመላው በመሠውያው ላይ አድርገህ አቃጥለው ይኸውም ለእግዚአብሔር የሚቀርብ ቍርባን ነው ። |
| ወትነሥእ ካልአ በግዐ ወያነብሩ አሮን ወደቂቁ እደዊሆሙ ላዕለ ርእሱ ። | ፲፱ | ሁለተኛውንም በግ አምጥተህ አሮንና ልጆቹ እጃቸውን በራሱ ላይ ይጫኑበት ። |

፳ ወሕርዶ ወንሣእ እምደሙ ወአንብር ዲበ ከተማ ዕዝኑ ለአሮን እንተ የማን ፤ ወዲበ ከተማ አጽባዕተ እዴሁ ዘየማን ፤ ወዲበ ከተማ አጽባዕተ እግሩ ዘየማን ወዲበ ከተማ ዕዘኒሆሙ ለደቂቀ አሮን ዘየማን፤ ወዲበ ከተማ አፃብዐ እደዊሆሙ ዘየማን ፤ ወዲበ ከተማ አጻብዐ እገሪሆሙ ዘየማን ።

በጉንም አርደህ አወራርደህ ከደሙ ቀድተህ አምጥተህ የአሮንን ቀኝ ጆሮውን፣ ቀኝ እጁን፣ ቀኝ እግሩን ቀበው፣ የአሮንም ልጆች ቀኝ ቀኝ ጆሮአቸውን፣ ቀኝ ቀኝ እጃቸውን ቀኝ ቀኝ እግራቸውን ቀባቸው ።

፳፩ ወትነሥእ እምደም ዘምሥዋዕት ፤ ወእምቅብዕ ቡሩክ፤ ወትነሰንስ ላዕለ አሮን ወላዕለ አልባሲሁ ፤ ወእምድኅሬሁ ላዕለ ደቂቁ ወላዕለ አልባሲሆሙ ወይትቄደስ ውእቱ ወዓራዙ ወደቂቁ ወዓራዚሆሙ ምስሌሆሙ ።

ከመሥዋዕቱም ደም ቀድሰህ ከናርኸው ከአራት ሽቱ ከአምስተኛ ዘይት አምጥተህ በአሮን ልብስ ላይ ርጨው ከሱም በኋላ በልጆቹና በልብሶቻቸው ላይ ርጭ፣ እሱም ይከብራል ልብሱም ልጆቹም ይከብራሉ ልብሶቻቸውም ።

፳፪ ወደሞ ለውእቱ በግዕ ትክዑ ውስተ ቤተ መቅደስ በዓውዱ ፤ ወትነሥእ እምውእቱ በግዕ ስብሐ ዘይገለብብ ከርሦ ወከብዶ ፤ ወከልኤተ ኵልያቶ ወስብሐ ዘላዕሌሆን ፤ ወትነሥእ አገዳሁ ዘየማን ፤ እስመ በእንተ ዝንቱ ይትፌጸም ።

የዚያንም በግ ደም በቤተ መቅደሱ በመሠውያው ዙርያ አፍስሰው፣ ከዚያም በግ ሆድ ዕቃውን የሚሸፍነውን ስብ ግልገል ጉበቱን ሁለት ኩላሊቶቹን በላያቸው ላይ ያለውን ስብንና የቀኝ ወርቹን ስብ አምጣ፣ የአሮን የክህነቱ ሥራ በዚህ ይፈጸማልና ።

፳፫ ወኅብስተ አሐተ ወጸሪቀ አሐተ እምውስተ መሶብ ዘውእቱ ንቡር ኵሉ ዘሚሙ ቅድመ እግዚአብሔር ።

(ሴዋውያን) በእግዚአብሔር ፊት አዘጋጅተው ከኖሩት በመሶብ ውስጥ ተቀምጦ ካለው አንድ እንጀራ አንድ ድፎ ቂጣ አምጣ ።

፳፬ ወታነብር ኵሎ ዘውስተ እዴሁ ለአሮን ፤ ወውስተ እደወ ደቂቁ፡ ወትፈልጦ ፍልጣነ በቅድመ እግዚአብሔር ።

ይህን ሁሉ አምጥተህ በአሮን እጅና በልጆቹ እጅ አኑረው ሁሉንም በእግዚአብሔር ፊት የተወደደ መሥዋዕት አድርገህ ለየው ።

፳፭ ወትትሜጠዎ እምእደዊሆሙ ፤ ወታነብር ዲበ ምሥዋዕ ለመዓዛ ሠናይ በቅድመ እግዚአብሔር ፤ መሥዋዕት ውእቱ ለእግዚአብሔር ።

ከሰጠኻቸውም በኋላ መልሰህ ከእጅ ከእጃቸው ተቀብለህ ለእግዚአብሔር በጎ መዓዛ ያለው መሥዋዕት ሊሆን በምሥዋዑ ላይ አቅርበው ይህም ለእግዚአብሔር በጎ መዓዛ ያለው መሥዋዕት ነው ። ዘሌዋ፣ ፰ ፳፰ ።

፳፮ ወትነሥእ ተላፆ ለበግዕ ዘፍጻሜ ለአሮን ፤ ወትፈልጦ ፍልጣነ በቅድመ እግዚአብሔር ወይኩን ለከ ክፍለ እምኔሁ ።

አሮን የተቀበበት የበጉንም ፍርንቢያ ወስደህ በእግዚአብሔር ፊት የተለየ መሥዋዕት አድርገው ፣ ከሱም ላንተ ዕድል ፈንታ ይሁንህ ። ዘኁ፣ ፲፰ ፲፩ ።

፳፯ ወመዝራዕቶኒ ትፈልጥ በከመ ፈለጥከ በግዐ ፍጻሜ እምኅበ አሮን ፤ ወእምኅበ ደቂቁ ።

አሮን ተቀብቶ የተሾመበት በጉን ከአሮንና ከልጆቹ እንደለየኸው ወርቹንም ከሥጋው ለየው ።

፳፰ ወይኩኖሙ ለአሮን ወለደቂቁ ሕገ ዘለዓለም በኀበ ውሉደ እስራኤል ፤ እስመ ፍልጣን ውእቱ ዝ ።

ይህ የተለየ መሥዋዕተ ኃጢአታቸው ነውና በእስራኤል ልጆች ዘንድ ለአሮንና ለልጆቹ ለዘለዓለሙ ሕግ (ሥርዓት) ይሁናቸው ። ዘሌ፣ ፲ ፲፭ ።

፳፱ ወፍልጣነ ይኩን በኀበ ውሉደ እስራኤል እምዝብኀት ዘይዘብሑ ለፍርቃኖሙ ፤ ፍልጣን ለእግዚአብሔር ።

ለእግዚአብሔር የተለየ መሥዋዕት ሁኖ ከመከራው ሊድኑበት ፭ኤል ከሚሠዉት መሥዋዕት ይልቅ በእስራኤል ልጆች ዘንድ ይህም ለአሮንና ለልጆቹ የተለየ መሥዋዕት ይሁናቸው ።

፴ ወልብሰ ቅድሳቲሁ ለአሮን ለይኩን ለውሉዱ እምድኅሬሁ ከመ ይትቀብዑ ቦቱ ፤ ወከመ ይፈጽሙ እደዊሆሙ ።

የአሮን ልጆች አራት ሽቱ አምስተኛ ዘይት አጣፍጠው እጆቻቸውን ተቀብተው ይከብሩበት ዘንድ ከሱ በኋላ አሮን የተሾመበት የአሮን ልብሰ ተክህኖ ለልጆቹ ይሁን ።

፴፩ ወሰቡዐ ዕለተ ለይልበሶ ካህን ዘህየንቴሁ እምደቂቁ፤ ዘይበውእ ውስተ ደብተራ ዘመርጡል ፤ ከመ ይሠየም በቅድሳት ።

ይህንም አሮን የተሾመበትን ልብሰ ተክህኖ በቅድስተ ቅዱሳን ሊሾም ወደ ደብተራ ኦሪት የሚገባው ከልጆቹ ስለሱ ተተክቶ የሚሾመው ካህን ሰባት ቀን ይልበሰው ።

፴፪ ወበግዐ ዘፍጻሜ ትነሥእ ወታበስል ሥጋሁ በመካን ቅዱስ ።

አሮንና ልጆቹ ከደሙ የተቀቡበት በጉን አርደህ አወራርደህ ሥጋውን ወስደህ በከበረ ቦታ ቀቅለው ።

፴፫ ወይብልዑ አሮን ወደቂቁ ሥጋ በግዕ ወኅብስተ ዘውስተ መሶብ በኀበ ኆኅተ ደብተራ ዘመርጡል ።

የበጉን ሥጋና በመሶብ ያለውን ድፎውን እምበሻውን አሮንና ልጆቹ በደብተራ ኦሪት ደጃፍ ተቀምጠው ይብሉት

፴፬ ይብልዕዎ በኀበ ተቀደሰ በህየ ከመ ይፈጽሙ እደዊሆሙ ፤ ለተቀድሶቶሙ ወውሉደ ባዕድ ኢይብልዖ እስመ

ሊከብሩበት ሊሾሙበት እጆቻቸውን እንዲቀቡ በዚያ በከበረ ቦታ ሁነው ይብሉት ፣ ነገር ግን የተቀደሰ ነውና፣

ቅዱስ ውእቱ ።

፴፭ ወለእመ ተርፈ እምሥጋ መሥዋዕት ዘፍጻሜ ወኅብስ ትኒ እስከ ደግደግ ታውዕዮ በእሳት ለዘተርፈ ወኢይትበ ላዕ እስመ ቅዱስ ውእቱ ።

፴፮ ወግበር ለአሮን ወለደቂቁ ከመዝ ኵሎ ዘከመ አዘዝ ኩከ ፡ ሰቡዐ ዕለተ ከመ ትረድም እደዊሆሙ ።

፴፯ ወላሕመ ዘእንበይነ ኃጢአት ትገብር ለለዕለቱ በዘበቱ ታነጽሕ ምሥዋዐ ሰበ ትቄድስ ቦቱ ።

፴፰ ወትቀብዖ ሰቡዐ ዕለተ ወታነጽሕ ለምሥዋዕ ወትቄ ድስ ፡ ወይኩን ምሥዋዒከ ቅዱሰ ቅዱሳን ፡ ወኵሉ ዘለከፎ ለውእቱ ምሥዋዕ ለይትቀደስ ።

፴፱ ወዝ ውእቱ ዘይትገበር ለመሥዋዕት ዘዘልፍ ፡ አባግዐ ንጹሐነ እለ እሐቲ ዓመቶሙ ፡ ክልኤተ ለለዕለቱ ።

፵ ወአሐደ በግዐ ትገብር በጽባሕ ፡ ወአሐደ ፍና ሠርክ ፡ ወዓሥራታ ለኢፍ ሥንዳሴ ልሑጽ በቅብዕ ፡ ወልቱም በራ ብዕታ ለኢን ፡ ወምጻሕተ ወይን ራብዕታ ለኢን ለአሐዱ በግዕ ።

፵፩ ወለካልእኒ በግዕ ዘትገብሮ ፍና ሠርክ በሐሳበ መሥ ዋዕትከ ዘነግህ ትገብሮ ።

፵፪ ወከማሁ ሞጻሕቶኒ ትገብሮ ለመዓዛ ሠናይ ፡ መሥዋ ዕት ውእቱ ለእግዚአብሔር ።

፵፫ ዘወትር ለትውልድክሙ ኀበ ኆኅተ ደብተራ ዘመር ጡል በቅድመ እግዚአብሔር በዘእትኤመር ለከ በህየ ከመ እንብብከ ።

፵፬ ወእኤዝዘሙ በህየ ለውሉደ እስራኤል ፡ ወእትቄደስ በክብርየ ።

፵፭ ወእቄድሳ ለደብተራ መርጡል ወለምሥዋዒሃ ፡ ወእቄ ድሶሙ ለአሮን ወለደቂቁ ከመ ይሠዑ ሊተ ።

፵፮ ወእኀድር ማእከሌሆሙ ለውሉደ እስራኤል ወእከውኖሙ አምላኮሙ ።

፵፯ ወየአምሩ ከመ አነ ውእቱ እግዚአብሔር አምላኮሙ ዘአውጻእክዎሙ እምድረ ግብጽ ከመ እሰመይ በላዕሌ ሆሙ ወእከውኖሙ አምላኮሙ ።

ምዕራፍ ፴ ።

፩ ወግበር ሊተ ምሥዋዐ ዘዕጣን እምዕፅ ዘኢይነቅዝ ዘእ መት ኑኁ ፡ ወእመት ራኅቡ ፡ ርቡዐ ግበሮ ፡ ወክዕበ እመት ቆሙ ፡ ወእምኔሁ ይትገበሩ አቅርንቲሁ ።

፪ ወትቀፍሎ ወርቀ ንጹሐ ምድሮ ወዓውደ አረፍቱ ፡ ወአቅርንቲሁ ወግበር ሎቱ ቀጸላ ዘወርቅ ።

(ከነገደ ሌዊ ያልተወለደ) ባዕድ አይብላው ።

ደሙን ከተቀቡበት ከበጉ መሥዋዕት ሥጋ ከድፎውም ከእምባሻውም እስከ ነገው ቢያድር ተርፎ ያደረውን በእ ሳት አቃጥለው የከበረ ነውና ፤ (ተርፎ አድሮ አይበላ) ።

እጆቻቸውን ትቀባቸው ዘንድ ቀባቸው ብዬ ያዘዝኩ ህን ሁሉ ለአሮንና ለልጆቹ ሰባት ቀን አድርግላቸው ።

ምሥዋዑን በምታከብርበት ደሙንም በምትቀባው ጊዜ ምሥዋዑን በምታነጻ ገንዘብ ስለ ኃጢአት የሚሠ ዋውን ላም ሰባት ቀን ዕለት ዕለት ሠዋው ።

በመሥዋዕት ኃጢአቱም ምሥዋዑን ሰባት ቀን ቀብ ተህ አንጻው አክብረው መሠውያህም ከከበሩ የከበረ ይ ሁን ፤ ምሥዋዑንም የነካው ሰው ሁሉ ይከብራል ።

(ጧት ማታ) ዘወትር ለመሥዋዕት የምትሠራው ሥራ ይህ ነው ፤ ንጹሐን (ማለት ቀንዳቸው ያልከረከረ ጥፍራ ቸው ያልዘረዘረ ላታቸው ያላረረ) ዓመት የሆናቸው ሁለት በጎች ።

አንዱን መሥዋዕተ ነግህ ፤ አንዱን መሥዋዕተ ሠርክ አድርገህ ሠዋቸው ፤ (ኢፍ አሥረ-ፈጅ ነው) ፤ ለመሥ ዋዕተ ነግህ የኢን መሥፈሪያ አራተኛ እጅ በሆነ ተወቅጦ በተንጣለለ ዘይት የተለወሰ ልዩ ጕርዶ የወጣለት የኢፍ አሥረኛውን ሥንዴ አቅርብ ፤ ለአንድ በግ ፍልቅ እድ ርገው ፤ የሚያፈሱት የኢን (የገንቦ) እርቦ ወይን ነው ።

በሠርክ የምታቀርበው ለሁለተኛውም በግ ፤ በነግህ በቀረብከው መሥዋዕት ልክ አድርገህ አቅርብለት ።

እንደዚሁም ፍልቅ አድርገው የሚያፈሱት ወይኑንም የገንቦ እርቦ ወይን አቅርብለት ፤ ይኸውም በጎ መዓዛ ያለ ው ሁኖ ለእግዚአብሔር የሚቀርብ መሥዋዕት ነው ።

ይኸውም አንተን ልነጋገርህ በምገለጥበት በታ በደብ ተራ አሪት ደጃፍ በእግዚአብሔር ፊት ዘወትር ለልጅ ልጆቻችሁ ጧት ማታ የሚቀርብ ይሁን ።

በዚያም በታ ሁኜ የእስራኤልን ልጆች አዛቸዋለሁ ፤ እኔም በክብሬ እመሰገናለሁ ።

ደብተራ ኦሪትንና መሠውያዋንም አከብራቸዋለሁ ለኔ ም ጧት ማታ መሥዋዕት እንዲሠዉልኝ አሮንና ልጆቹን አከብራቸዋለሁ ። ዘሌ ፳፩ ፲፭ ።

(እኔም) በእስራኤል ልጆች (በረድኤት) አድሬባቸው እኖራለሁ የፍቅር አባትም እሆናቸዋለሁ ።

በነሱ እጠራባቸው ዘንድ ከግብጽ አገር ያወጣኋቸው ፈጣሪያቸው እግዚአብሔር እንደሆንኩና ፤ (የፍቅር የሃይ ማኖት) አባታቸው እንደሆንኩም ያውቃሉ ።

ምዕራፍ ፴ ።

(ሸምሸር ሰጢን ከሚባል) ከማይነቅዝ ዕንጨት የዕጣን መሠውያ (ማዕጠንት) ሥራልኝ ይህንንም አቈልቋዩን ክን ድ ፤ ወርዱን ክንድ ፤ ምዕዙን አድርገህ ሥራው ፤ ቁመቱም ሁለት ክንድ ይሁን ፤ ቀንዶቹም ሥረ-ወዕ ይሁኑ ።

ምድሩን የግድግዳውን ዙርያና ቀንዶቹንም የጸራ ወርቅ ለብጣቸው ፤ በዙርያውም የወርቅ ከንፈር (ክፈፍ) አድርግበት ። ዘፀ ፴፯ ፳፭ ፤ ፴ ፭ ።

፬ ወግበር ሎቱ ክልኤተ አውቃፋተ ወርቅ መትሕተ ቀጸላሁ፤ ላዕለ ክልኤቱ ፍናሁ፤ ወትገብር ላዕለ ክልኤቱ ገበዋቲሁ።

ከክንፈሩም በታች ሁለት የወርቅ እምብርች አድርግ ለት፤ እነዚህንም በሁለት ጐኖቹ አድርጋቸው። ዘፀ፡ ፴፯ ፳፮፡ ፵ ፩።

፭ ወይኩኑ አብያተ ለመፃውሪሁ ከመ ያንሥኡ በሙ ኪያሁ።

እሱንም በእነሱ እንዲያነሡባቸው ለመሸከሚያዎቹ ቤት ይሁኑ። ራዕ ዮሐ፡ ፰ ፫።

፮ ወግበር መፃውርተ እምዕፀ ዘኢይነቅዝ፤ ወቅፍሎሙ ወርቀ።

ከማይነቅዝ ዕንጨት እምቀተህ መሸከሚያዎችን አድርግለት ወርቅንም ለብጣቸው።

፯ ወታነብሮ ቅድመ መንጦላዕት ዘሀሎ ዲበ ታቦት ዘመርጡል በዘእትኤመር ለከ በህየ።

ማዕጠንቱንም እኔ ላንተ በዚያ በምገለጥልህ በታ በደብተራ ኦሪት ካኅቹ ታቦት በላይ ባለ መጋረጃ አንጻር አኑረው። ፩ ነገ፡ ፳፫ ፲፫፤ ሉቃ፡ ፩ ፱።

፰ ወይዕጥን በውስቴቱ አሮን ዕጣነ ዘቅታሬ ድቁቀ በበ ነግህ።

አሮን በጎ መዓዛ ያለው የተፈጨ የደቀቀውን ዕጣን በነግህ በነግህ ይጠንበት። ፩ ሳሙ፡ ፪ ፳፰።

፱ ወሶበ ይገብር መኅትወ በሠርክ ይዕጥን በውስቴቱ ዘዘልፍ በቅድመ እግዚአብሔር በትውልድክሙ።

በዓልም በደረገ ጊዜ በዋዜማው ለልጅ ልጃችሁ መጠበቂያ ሊሆን በእግዚአብሔር ፊት ዘወትር በሠርክ በሠርክ ይጠንበት። ዘሌዋ፡ ፲ ፩።

፲ ወኢትደምሩ ውስቴቱ ዕጣነ ዘካልእ ቅታሬሁ፤ ወመሥዋዕተ ወሞጻሕተ ኢታውጽሑ ዲቤሁ።

ቅታሬ መዓዛው ልዩ የሆነ ሌላ ዕጣን አትጨምሩበት በማዕጠንቱም መሥዋዕት አትጠኑበት፤ ወይንንም ፍልቅ አድርጋችሁ በላዩ ላይ አታፍስሱበት።

፲፩ ወይትመሐለል አሮን በአቅርንቲሁ ለለዓመት ምዕረ፤ ወይነሥእ እምደም ዘያነጽሕ ኃጢአተ ምዕረ ለለዓመት፤ ወይገብር ከመ ያንጽሕ ትውልዶሙ ወቅዱሰ ቅዱሳን ውእቱ ለእግዚአብሔር።

አሮን ከዓመት አንድ ጊዜ አቅርንተ ምሥዋዑን ይዞ ይጸልይ፤ ከዚያም አስቀድሞ የሕዝቡን ኃጢአት ከሚያስተሠርየው ከመሥዋዕተ ደም ይዞ ከዓመት አንድ ጊዜ ይግባ፤ የጅኤል ነገዳቸው ከኃጢአታቸው ያነጻበት ዘንድ በዓለ አስተሥርዮን ያድርግ፤ ይኸውም ደሙ ዕጣኑ ለእግዚአብሔር በጎ መዓዛ ያለው መሥዋዕት ሁኖ የሚቀርብ ከከበሩ የከበረ ነው። ዘሌዋ፡ ፳፫ ፳፯።

፲፩ ወነበበ እግዚአብሔር ለሙሴ ወይቤሎ፤ ለእመ ነሣእከ ሐሊናሆሙ ለውሉደ እስራኤል ከመ ትኈልቆሙ ለየሀብ ኣሐዱ አሐዱ ቤዛ ነፍሱ ለእግዚአብሔር።

እግዚአብሔርም ሙሴን እንዲህ ብሎ ተናገረው፤ የእስራኤልን ልጆች ልቡና ይዘኸው እንደሆነ አንዱም አንዱ ለእግዚአብሔር ገንዘቡን ለሰውነቱ ቤዛ አድርጎ ይስጥ።

፲፪ ወኢይምጽእ ላዕሌሆሙ ድቀት አመ ትኋልቆሙ።

ይህን ካደረጉ በኋላ በቈጠርኻቸው ጊዜ መቅሠፍቱ በነሱ ላይ አይመጣባቸውም። ፪ ሳሙ፡ ፳፬ ፪።

፲፫ ወዝ ውእቱ ዘይሁቡ ኵሎሙ እለ የሐውሩ ከመ ይትኈለቁ፡ መንፈቃ ለሰቅል በሰቅል ቅዱስ ዕሥራ አበሊ ሰቅል፤ ወመንፈቃ ለሰቅል ቍርባኑ ለእግዚአብሔር።

ሊቈጠሩ የሚሄዱትም ሰዎች ሁሉ የሚሰጡት ይህ ነው እንደ መቅደሱ ሚዛን የሰቅል ግማሽ ነው፤ ይኸውም የሰቅል ግማሽ ሃያ አበሊ (አቦት) ነው፤ የሰቅሉም ግማሽ ለእግዚአብሔር የተወደደ ሁኖ የሚቀርብ ቍርባኑ ነው።

፲፬ ወኵሉ ዘየሐውር ከመ ይትኈለቍ ዘእምዕሥራ ክራማቲሁ፤ ወረድፋደ።

ሊቈጠርም የሚሄደው ሁሉ ሃያ ዓመት የሆነው ከሃያም ዓመት በላይ የሆነው ነው።

፲፭ ብዑል ኢይወስክ፤ ወነዳይ ኢያንትግ እመንፈቃ ለሰቅል፤ እለ ያበውኡ ቍርባኖሙ ለእግዚአብሔር ቤዛ ነፍሶሙ።

ለሰውነታቸው መበዣ ሊሆን ለእግዚአብሔር ቍርባን አድርገው ከሚያገቡት ከድሪም (አቀመት) አትርፎ ባለጸጋም አይጨምር ድኻም አያጕድል። ኢዮብ ፴፬ ፲፱።

፲፮ ወትነሥእ ብሩረ ዘአብኡ ቍርባኖሙ ውሉደ እስራኤል፤ ወትሁቦ ለምግባረ ደብተራ ዘመርጡል፤ ወይኩኖሙ ተዝካሮሙ ቅድመ እግዚአብሔር ቤዛ ነፍሶሙ።

የእስራኤልም ልጆች ቍርባን አድርገው ያገቡትን ብር ተቀብለህ ለደብተራ ኦሪት ሥራ ሊሆን (ለአሮን) ስጠው፤ ይኸውም በእግዚአብሔር ፊት መታሰቢያ ሊሆናቸው ለሰውነታቸው ቤዛ ነው። ዘኍ፡ ፲፯ ፵።

፲፯ ወነበበ እግዚአብሔር ለሙሴ ወይቤሎ፤ ግበር መቅለደ ዘብርት፤ ወመንበሩሂ ዘብርት።

እግዚአብሔር ሙሴን ተናገረው እንዲህም አለው፤ የብርት መታጠቢያ ሰን (ሥስሥት) ሥራ መቀመጫውም ብርት ይሁን።

፲፰ ወታነብሮ ማእከለ ደብተራ ዘመርጡል ወማእከለ ምሥዋዕ ወትሠውጥ ውስቴቱ ማየ።

ይህንም በምሥዋዐ ብርቱና በደብተራ ኦሪት መካከል አኑረው ውኃም ጨምርበት።

፲፱ ወይትሐፀቡ አሮን ወደቂቁ እምውስቴቱ እደዊሆሙ

አሮንና ልጆቹም መሥዋዕትን ለመሠዋት ወደ ደብ

ወእገሪሆሙ፡ ሶበ ይበውኡ ውስተ ደብተራ መርጡል ከመ ይሡዑ ።

፳ ወሶበ የዓርጉ ይሡዑ መሥዋዕተ ለእግዚአብሔር ይትሐፀቡ እደዊሆሙ ወእገሪሆሙ ከመ ኢይሙቱ ።

፳፩ ወይኩኖሙ ሕግ ዘለዓለም ሎሙ ወለውሉዶሙ እምድኅሬሆሙ ።

፳፪ ወነበበ እግዚአብሔር ለሙሴ ወይቤሎ፡ አንተ ንሣእ አፈዋተ ጽጌ ዘከርቤ ቅድወ ኃምስተ ምእተ ሰቅለ ።

፳፫ ወቀናንሞ ቅድወ በመንፈቁ ለቅዳሚ ክልኤተ ምእተ ወኃምሳ፡ ወቀጺመተ ቅድወ ክልኤተ ምእተ ወኃምሳ ።

፳፬ ወአበሚ ኃምስተ ምእተ በሰቅል ቅዱስ፡ ወቅብዐ ዘይት በመስፈርተ ኢን ።

፳፭ ወግበር ቅብዐ ቅዱሰ ጽዑጠ ዘጸዓጢ ።

፳፮ ወትቀብዖ እምኔሁ ለደብተራ ዘመርጡል፡ ወለታቦተ መርጡል ።

፳፯ ወማእደ ወኵሉ ንዋዮ፡ ወለተቅዋመ ማኅቶት ወለኵሉ ንዋያ፡ ወለምሥዋዕኒ ዘዕጣን ።

፳፰ ወለምሥዋዕ ዘመሥዋዕት ወለኵሉ ንዋዩ፡ ወለመቀለድ ምስለ መንበሩ ።

፳፱ ወትቄድሶሙ ወይከውኑ ቅዱሳነ፡ ወዘኪያሆሙ ለከፈ ለይትቀደስ ።

፴ ወለአሮን ወለደቂቁ ቅብዖሙ ወቀድሶሙ፡ ከመ ይሡዑ ሊተ ።

፴፩ ወበሎሙ ለውሉደ እስራኤል፡ ዝ ቅብዕ ዘይትቀብዑ ቅዱስ ለይኩን ማእከሌክሙ ለትውልድክሙ ።

፴፪ ወበዕድ ሰብእ ኢይትቀበዕ እምኔሁ፡ ወከመ አምሳሊሁ ኢትግበሩ ለክሙ ከማሁ፡ እስመ ቅዱስ ውእቱ ዝ ቅብዕ አመ ትገብርዎ ።

፴፫ ወዘወሀበ እምኔሁ ለባዕድ ዘመድ ለይሠሮ እምሕዝቡ ።

፴፬ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለሙሴ፡ ንሣእ ለከ አፈዋተ ማየ ልብን ወቀንአተ ቅድወ ወስኂነ ዘያንጸበርቅ፡ ወኵሉ ዕሩየ ለይኩን ድልወቱ ።

፴፭ ወግበርዎ ዕጣነ ኪያሁ ግብረ ዕጣን ቅድወ ወግብረ ንጹሐ ወቅዱሰ ግበር ።

፴፮ ወተሐርጽ እምኔሁ ድቁቀ ወታንብሮ ቅድመ ደብተራ ዘመርጡል፡ በዘበቱ እትኤመር ለከ እምህየ ወቅዱሰ ቅዱሳን ለይኩንክሙ ዝ ዕጣን ።

፴፯ ወበዝ ግብረት ኢትግበሩ አርአያ ዝ ዕጣን ኀፋሙ ለይኩንክሙ ዝንቱ፡ ወቅዱስ ለእግዚአብሔር ።

ተራ ኦሪት በገቡ ጊዜ በብርት ከለው ውኃ እጃቸውንና እግራቸውን ይታጠቡ ። ኢሳ፡ ፶፪ ፲፩ ።

ለእግዚአብሔር መሥዋዕትን ለማሳረግ ወደ ደብተራ ኦሪት በገቡ ጊዜ እንዳይሞቱ (እንዳይቀሠፉ) እጃቸውንና እግራቸውን ይታጠቡ ። ዕብ፡ ፲ ፳፪ ።

ይህም ለጊዜው ለነሱ ከነሱም በኋላ ለልጅ ልጆቻቸው ለዘለዓለሙ ሕግ ሥርዓት ይሁናቸው ።

እግዚአብሔር ሙሴን እንዲህ ብሎ ተናገረው፤ ከማረ ከተወደደ ከርቤ ከሚባል ሽቱ አበባ የጣፈጡ ሽቶዎቹን አምስት መቶ ወቄት ምዝን አንተ ተቀበል ።

ያማረ የተወደደ ቀናንሞ የሚባል ሽቱንም በቀደመው ሽቱ እኩሌታ ሁለት መቶ አምሳ ወቄት ተቀበል ያማረ የተመረጠ ቀጺመት የሚባል ሽቱንም የሁለት መቶ አምሳ ወቄት ምዝን ተቀበል ።

አበሚ የሚባለውንም ሽቱ በቅዱስ ሰቅል ሚዛን አምስት መቶ ወቄት ምዝን ተቀበል፡ የወይራ ዘይትንም በግድጋ አከፋይ አንድ የኢን መሥፈሪያ ተቀበል ።

ይኸንንም አዋቂ ያጣፈጠው የተቀደሰ ሽቱ አድርገው ።

ከዚህም ደብተራ ኦሪትን ቀባት፡ በደብተራ ኦሪት ውስጥ ያለች ታቦቲቱንም ። ዘኍ፡ ፯ ፩ ።

ገበታውንም የገበታውንም ዕቃ ሁሉ ፋና የሚበራበት መቅረዙንም ዕቃውንም ሁሉ ዕጣን የሚታጠንበት ማዕጠንቱንም ቅባ ። ዘሌዋ፡ ፰ ፲ ።

መሥዋዕቱ የሚሠዋበት መሠውያን ዕቃውንም ሁሉ የብርቱ ማስታጠቢያውን ሰን ከመቀመጫው ጋር ቅባው ።

በዚህ ሁሉ አክብራቸው እነሱም የተቀደሱ ይሁኑ እነሱንም የነካቸው የተቀደሰ ይሁን ።

አሮንና ልጆቹን ለኔ መሥዋዕት እንዲሠዉልኝ ቀብተህ አክብራቸው ።

የእስራኤልን ልጆች ይህ የሚቀቡት ሽቱ ለልጅ ልጃችሁ ዘመን በናንተ በሌዋውያን መካከል የተለየ ይሁን እናንተ አትቀቡት በላቸው ።

ይህንም ስታደርጉት ከእስራኤል ያልተወለደ ሌላ ሰው ከሱ አይቀባ፡ እንደሱም አስመስላችሁ አሁን እንደተናገርኩት ለራሳችሁ አታድርጉ ይህ ሽቱ የተቀደሰ ነውና ።

ከዚህ ሽቱ ዘመዴ ነው ብሎ ለባዕድ ዘመድ የሰጠ ከወገኑ ተለይቶ ይጥፋ (በድንጋይ ተወግሮ) ይሙት ።

እግዚአብሔርም ሙሴን ልበንጃ ሽቱ ያማረ የተወደደ ቀንአት የተባለ ሽቱ የሚያበራ ነጭ ዕጣን ከእስራኤል ተቀበል፡ ሚዛኑም ሁሉ የተካከለ ይሁን ።

ይህንንም ያማረ የተወደደ የዕጣን ሥራ አድርጋችሁ ሠርታችሁ ዕጣን አድርጉት፡ የከበረና የጸራ ሥራ አድርገህም ሥራው ። ዘፀ፡ ፳፱ ፵፪ ።

ከዚህም ዕጣን ወስደህ ፈጭተህና አድቅቀህ ዱቄቱን ከዚያ ላንተ በምገለጥበት በታ በደብተራ ኦሪት ፊት አኑረው፡ ይህም ዕጣን ለናንተ ከከበሩ የከበረ ይሁንላችሁ ።

የዚህንም ዕጣን አምሳያ በበታችሁ ሠርታችሁ አታድርጉ፡ ይህም ለናንተ እርም ይሁንባችሁ፡ ለእግዚአብሔር ግን የከበረ የተለየ ገንዘቡ ይሁን ።

፴፭ ወዘአግበረ እምኔሁ ከመ ያጼንዎ ፡ ለይማስን እም ሕዝቡ ።

ምዕራፍ ፴፮ ።

፩ ወነበበ እግዚአብሔር ለሙሴ ወይቤሎ ፡ ናሁ ተሰመይኩ በስሙ ለበስልኤል ወልደ ኡሬ ፡ ወልደ ሑር ዘእምነገደ ይሁዳ ።

፪ ወመላእክዎ መንፈሰ ቅዱሰ ፡ ወጥበበ ወአእምሮ ፡ ወአቁም በኵሉ ምግባር ከመ የሐሊ ።

፫ ወይኩን ሊቀ ጸረብት ፡ ወከመ ይግበር ወርቀ ወብሩረ ወብርተ ፡ ወግብረ ያክንት ፡ ወግብረ ሕብድ ፡ ወለይ ከዐብ ፡ ወቢሶስ ክዐብ ።

፬ ወግብረ እብንሂ ዘይትገበር ውስተ ምግባር ፡ ወዘይጸርብ እምዕፅ ፡ ከመ ይግበር እምኵሉ ግብር ።

፭ ወአነ ወሀብኩ ኤልያብሃ ወልደ አክሴምክ ፡ ዘእምነገደ ዳን ።

፮ ወለኵሉ ጠቢበ ልብ ወሀብኩ አእምሮ ወይግበር ኵሎ ዘአዘዝኩከ ።

፯ ደብተራ ዘመርጡል ፡ ወታቦተ ዘኪዳን ፡ ወምሕዋዐ ዘላዕሌሃ ፡ ወንዋየ ለደብተራ ።

፰ ወምሥዋዐ ዘዕጣን ወተቅዋመ ማኅቶት ንጽሕት ፡ ወኵሉ ንዋያ ፡ ወማእደ ወኵሉ ንዋዮ ፡ ወምሥዋዐ ዘመሥዋዕት ፡ ወኵሉ ንዋያቲሁ ወማእከከ መመንበሮ ።

፱ ወአልባሲሁኒ ዘክብሩ ለአሮን ፡ ወአልባሰ ደቂቁ ብዘ ቦቱ ይገብሩ ሊተ ግብረ ።

፲ ወቅብዐ ዘይትቀባዕ ፡ ወዕጣነ ዘየዓጥኑ ለመቅደስ ፡ ወኵሎ ዘአዘዝኩከ ይግበሩ ።

፲፩ ወነበበ እግዚአብሔር ለሙሴ ወይቤሎ አንተ አዝዞሙ ለደቂቀ እስራኤል ።

፲፪ ወበሎሙ ዑቁ ከመ ትዕቀቡ ሰንበትየ ሕስመ ትእምርት ውእቱ በኀቤየ ወበኀቤክሙኒ ወበትውልድክሙ ከመ ታእምሩ ከመ አነ ውእቱ እግዚአብሔር ዘእቄድሰክሙ ።

፲፫ ወዕቀቡ ሰንበትየ እስመ ቅድስት ይእቲ ለክሙ ፡ ወዘአርኰሳ ሞተ ለይሙት ።

፲፬ ወኵሉ ዘይገብር በቲ ግብረ ለትሥሮ ይእቲ ነፍስ እምሕዝባ ።

፲፭ ሰዱሰ ዕለተ ትገብር ግብረከ ፡ ወሳብዕት ዕለት ሰንበት ዕረፍት ወቅድስት ለእግዚአብሔር ፡ ወኵሉ ዘይገብር ግብረ በዕለተ ሰንበት ፡ ሞተ እሙዊት ለይሙት ።

፲፮ ወይዕቀቡ ደቂቀ እስራኤል ሰንበተ ፡ ከመ ይግበሩ በት ውልዶሙ ሥርዓት ይእቲ ለዓለም ሊተ ።

፲፯ ወለደቂቀ እስራኤል ትእምርት ውእቱ ዘለዓለም ፡ እስመ በሰዱስ ዕለት ገብረ እግዚአብሔር ሰማየ ወምድረ ወበሳብዕት ዕለት ፈጸመ ወአዕረፈ ።

ከዚህም ዕጣን በቤቱ ተድላ ደስታ ሊያደርግበት ሊያሸተው (እንደ ቤተ እግዚአብሔር አድርጎ) የሠራ ሰው ከወገኖቹ ተለይቶ ይጥፋ (በእሳት ተቃጥሎ) ።

ምዕራፍ ፴፮ ።

እግዚአብሔር ሙሴን እንዲህ ሲል ተናገረው ፤ እነሆ በበስልኤል ስም ተጠራሁ ፡ ይህም ከነገደ ይሁዳ የተወለደ የሑር የልጅ ልጅ የኡሬ ልጅ በስልኤል ነው ።

መንፈስ ረድኤትን ጥበብን ዕውቀትን ሞላሁበት (አሳደርሁበት) እሱም በሥራው ሁሉ የተወሰነ ነው ።

ብልህ ጋበዝ አምበ (የአናጢዎች አለቃ) ተሹሞ ሐስበ ወርቁን ብሩን ብርቱን ሰማያዊ ሐሩን ብሩ ሐሩን ዕጽፍ ሁኖ የተፈተለ ቀይና ነጭ ሐሩን ይሠራ ዘንድ ነው ።

በሥራው ሁሉ ተጠርቦ ተለዝቦ የሚሠራ የዲንጋይም ሥራ ከዕንጨትም ወገን የሚጠርበውንና የሚያለዝበውን የዕንጨቱን ሥራ ከሥራ ሁሉ ለይቶ ይሠራ ዘንድ ነው ።

እኔም ከነገደ ዳን የሚሆን የአክሴምክ ልጅ ኤልያብን ሰጠሁ ። ፩ ነገ ፯ ፲፬ ። ኢሳ ፳፰ ፳፮ ።

ያዘዝኩህን ሁሉ ይሠሩ ዘንድ በልቡናቸው ጥበብን እውቀትን ላሳደርሁባቸው ሁሉ እውቀትን ሰጠኋቸው ።

ደብተራ ኦሪትን ሥርዓት ጸንቶበት የሚኖር ታቦቱን መክደኛዋን የደብተራ ኦሪትን ዕቃ ይሠሩ ዘንድ ዕውቀትን ሰጠኋቸው ። ዘፀ ፡ ፴፫ ፴፬ ።

ዕጣን የሚታጠንበት ማዕጠንትን ፋናው የሚበራበት የነጻውን መቅረዝ ዕቃውን ሁሉ ገበታውንና ዕቃውን ሁሉ መሥዋዕቱ የሚሠዋበት መሠዊያውንና ዕቃዎቹን ሁሉ መቀለጸንና መቀመጫውን ይሠሩ ዘንድ ።

አሮን የሚከበርባቸውን ልብሶች የክህነት ሥራ በሚሠሩ ልጆች ገንዘብ የልጆቹንም ልብሶች ይሠሩ ዘንድ ።

የሚቀቡትን ቅብዐ ክህነት ለቤተ መቅደስ የሚያጥኑትን ዕጣን ሊሠሩትም ያዘዝሁትን ሁሉ ይሠሩ ዘንድ ዕውቀትን ሰጠኋቸው ።

እግዚአብሔር ሙሴን እንዲህ ብሎ ተናገረው ፤ አንተ የእስራኤልን ልጆች (እንዲህ ብለህ) እዘዛቸው ።

የማከብራችሁ እኔ እግዚአብሔር እንደሆንኩ ታውቁ ዘንድ በኔና በናንተ ዘንድ ለልጅ ልጃችሁ ምልክት ነውና ሰንበቶቼን ፈጽማችሁ ጠብቁ በላቸው ።

ለናንተ የከበረች (በዓል) ስለሆነች ቅዳሜን አክብሯት የሻራትም ሰው ፈጽሞ ይሙት ።

ሥራውንም የሚሠራበት ሁሉ ያች ሰውነት ከወገኖቿ ተለይታ ትጥፋ ። ዘሌዋ ፳፮ ፪ ፡ ሕዝ ፵፬ ፳፬ ።

ስድስት ቀን ሥራህን ሥራ ፡ ሰባተኛው ቀን ግን ለእግዚአብሔር የተቀደሰች በዓል ናትና ቅዳሜ ቀን ሥራን የሚሠራ ሁሉ ፈጽሞ ይሙት ።

በልጅ ልጆቻቸው ይሠሩት ዘንድ የእስራኤል ልጆች ቅዳሜን ያክብሩ ፡ ለኔም የዘለዓለም ሥርዓቴ ናት ።

ለእስራኤልም ልጆች ለዘለዓለም የገዘና የተገኘ ምልክታቸው ነው እግዚአብሔር በስድስተኛው ቀን ሰማይንና ምድርን ፈጥሮ በሰባተኛይቱ ቀን (ቅዳሜ) ሥራውን

፲፰ ወሶበ ፈጸመ ተናግሮ ምስሌሁ በደብረ ሲና ወሀበ ለ
ሙሴ ክልኤተ ጽላተ ዘትእዛዝ ፣ ጽላት ዘእብን ፣ ጽሑፋት
በአጽባዕተ እግዚአብሔር ።

ምዕራፍ ፴፪ ።

፩ ወሶበ ርእዩ ሕዝብ ከመ ጐንደየ ሙሴ ወሪደ እምደ
ብር ተንሥኡ ላዕለ አሮን ወይቤልዎ ግበር ለነ አማልክተ
እለ የሐውሩ ቅድሜነ እስመ ዝኩ ብእሲ ሙሴ ዘአውጽ
አነ እምድረ ግብጽ ኢነአምር ምንተ ኮነ ።

፪ ወይቤሎሙ አሮን ንሥኡ ሠርጐ ወርቅ ዘውስተ አዕ
ዛነ አንስቲያክሙ ወአዋልዲክሙ ወአምጽኡ ኀቤየ ።

፫ ወነሥኡ ኵሉ ሕዝብ ሠርጐ ወርቅ ዘውስተ አዕዛነ
አንስቲያሆሙ ወአምጽኡ ኀበ አሮን ።

፬ ወተመጠወ እምእደዊሆሙ ወመሰሎ በምስል ወገ
ብሮ ላሕመ ዘስብክ ወይቤሎሙ እሉ አሙንቱ አማል
ክቲከ እስራኤል ዘአውጽኡከ እምድረ ግብጽ ።

፭ ወሶበ ርእየ አሮን ነደቀ ምሥዋዐ አንጻሮ ወአዖደ እን
ዘ ይብል በዓለ እግዚእ ጌሠም ።

፮ ወጌሠ አሮን በማኅታ ወአዕረገ መሥዋዕተ ወአብአ
ቍርባነ ዘመሥዋዕተ ፍርቃን ፣ ወነበሩ ሕዝብ ይበልዑ
ወይሰትዩ ወተንሥኡ ይዘፍኑ ወይትዋነዩ ።

፯ ወነበበ እግዚአብሔር ለሙሴ ወይቤሎ ሑር ወአፍጥን
ወሪደ እምዝየ ፣ እስመ አበሱ ሕዝብከ ዘአውጻእከ እም
ድረ ግብጽ ።

፰ ወወጽኡ እምፍኖት ዘአዘዝክዎሙ ወገብሩ ላሕመ
ወሰገዱ ወሦዑ ሎቱ ወይቤሉ ፣ እሉ እሙንቱ አማልክ
ቲከ እስራኤል ዘአውጽኡከ እምድረ ግብጽ ።

፱ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለሙሴ ፣ ርኢኩ ዘንተ ሕዝበ
ወናሁ ዝንቱ ሕዝብ ግዙፈ ክሣድ ።

፲ ወይእዜኒ ኅድገኒ እትመዓዕ በመዓትየ ፣ ወእሠይጦሙ
ላዕለ ሕዝብ ክቡድ ወዓቢይ ።

፲፩ ወሰአለ ሙሴ ቅድመ እምላኩ ወይቤ ለምንት እግዚኦ
መዓተ ትትመዓዕ ላዕለ ሕዝብከ ዘአውጻእከ እምድረ ግብጽ
በኃይል ጽኑዕ ወበመዝራዕት ልዑል ወዐቢይ ።

፲፪ ከመ ኢይበሉ ግብጽ በእኩይ አውጽኦሙ ከመ ይቅ
ትሎሙ በውስተ አድባር ወከመ ያጥፍኦሙ እምድር ፣ አቍ
ርር መዓትከ ዘተማዕከ ወመሐሬ ኵነ ላዕለ እከዮሙ ለሕ
ዝብከ ።

፲፫ ተዘከር አብርሃምሃ ወይስሐቅሃ ወያዕቆብሃ አግብርቲከ
ዘመሐልከ ሎሙ በርእስከ ወትቤሎሙ ፣ ብዙኀ አበዝኆ
ለዘርእክሙ ከመ ከዋክብተ ሰማይ ብዙኀ ፣ ወኵሎ ዘንተ
እሁብ ለዘርእክሙ ወይመልክዋ ለዓለም ።

፲፬ ወሠረየ እግዚአብሔር በእንተ እኪት ዘይቤ ይግበር

ፈጽሞ ዐርፎብታልና ።

በደብረ ሲና ከሱ ጋራ ተናግሮ ከጨረሰ በኋላ ዐሥሩ
ቃላት የተጻፈበቸው ሁለቱን ጽላት ለሙሴ ሰጠው ፣ እነዚ
ህም በእግዚአብሔር ጣት በእብን በረድ የተጻፉ ናቸው ።

ምዕራፍ ፴፪ ።

ሕዝቡም ሙሴ ከደብረ ሲና መውረዱን እንደ ዘገየበ
ቸው በዩ ጊዜ ከግብጽ አገር ያወጣን ወንድምህ ሙሴ
ምን እንደ ሆነ አናውቅምና ፣ በፊታችን የሚሄዱልን ጠላ
ቶቻችንን የሚያጠፉልን አማልክትን ሥራልን ብለው በአ
ሮን ላይ (በጠላትነት) ተነሡበት ። ዘዳግ፣ ፱ ፪ ።
አሮንም በሚስቶቻችሁና በሴት ልጆቻችሁ ጆሮዎች
ያለ የወርቅ ጌጣ - ጌጥ ተቀብላችሁ ወደኔ አምጡ አላቸው ።
ሕዝቡም ሁሉ በሚስቶቻቸው ጆሮ የነበረውን የወርቅ
ጌጣ - ጌጥ ሰብረው ወደ አሮን አመጡ ።
(አሮንም) ከእጃቸው ተቀብሎ በመቀረጫ ቀረጸው ፣
ቀልጦ የተሠራ ጥጃም አድርጎ እስራኤል !! ከግብጽ አገር
ያወጡህ አማልክቶችህ እሊህ ናቸው አላቸው ።
አሮንም ወደው እንደተቀበሉት ባየ ጊዜ በጣዖቱ
ፊት ለፊት መሠውያን ጸፈጸፈ ፣ (ወድያውም) ነገ የጌታ
በዓል ነው ብሎ አዋጅ አስነገረ ። ፩ ነገ፣ ፲ ፳ ።
አሮንም በነጋታው ማለዳ ተነሥቶ መሥዋዕቱን አሰረገ
ከመከራ የሚድኑበት ቍርባንም አቀረበ ፤ ሕዝቡም
(በጣዖቱ አጠገብ ተቀምጠው) ተረፈ መሥዋዕቱን ሊበሉ
ሊጠጡ ሊዘፍኑ ሊጫወቱ ተነሡ ። ፩ ቆሮ፣ ፲ ፯ ።
እግዚአብሔርም ሙሴን እንዲህ ብሎ ተናገረው !
ከግብጽ አገር ያወጣኻቸው ወገኖችህ በድለዉኛልና ከዚህ
(ከደብረ ሲና) ፈጥነህ ወርደህ ሂድ ።
እኔ ከዘዝኋቸው ሕግ ሥርዓት ወጥተው በደሉ የላሙ
ንም ምስል ሠርተው አቁመው ሰገዱለት ፣ መሥዋዕቱንም
ሠዉለት ፣ እስራኤል ከግብጽ ያወጡህ አማልክቶችህም
እነሂ ናቸው አሉ ። ፩ ነገ፣ ፲፪ ፳፰ ።
እግዚአብሔር ሙሴን ይህን ሕዝብ አየሁት እነሆም
አንገተ ደንዳና ሕዝብ ነው ። ኢሳ፣ ፵፰ ፬ ።
አሁንም ተቈጥቼ ላጥፋቸው ተወኝ ከዚህ በሚበል
ጥና በሚበዛ ወገን ላይ እሾምኻለሁ አለው ።
ሙሴም በፈጣሪው ፊት ቁሞ ጸለየ (ለመነ) አቤቱ ከግ
ብጽ አገር በጽኑ ኃይል በልዑልና በታላቅ ሥልጣን ያወ
ጣኻቸው ወገኖችህን ለምን ተቈጥተህ ታጠፋቸዋለህ አለ ።
የግብጽ ሰዎች በተራራው ሊገድላቸው ከዚህ ዓለም
ሊያጠፋቸው (ወገኖቹ እስራኤልን) በክፉ ነገር አወጣቸው
እንዳይሉ የተቈጣህባቸውን ቁጣ አብርድላቸው የወገኖች
ህንም በደል ይቅር በይ ሁን (ይቅር በል) ።
ከነዓንን ለዘለዓለሙ ሊገዟትና ሊወርሱዋት ዘራች
ሁን እንደ በዙ እንደ ሰማይ ከዋክብት አበዛዋለሁ ፣ ይህን
ንም ሁሉ ለልጆቻችሁ እሰጣቸዋለሁ (ሕያው የ አሜንየ
ብለህ) በራስህ የማልክላቸው አገልጋዮችህ አብርሃም ይስ
ሐቅ ያዕቆብን አስብ ። ዕብ፣ ፲፯ ፲፫ ።
እግዚአብሔርም በሕዝቡ ላይ አደርጋታለሁ ብሎ የተ

ላዕለ ሕዝብ ።

፲፭ ወተመይጠ ሙሴ ወወረደ እምደብር ወክልኤ ጽላት ዘትእዛዝ ዘውስተ እደዊሁ ፡ ጽላት ዘእብን ወጽሑፋት እንተ ክልኤቱ ገበዋቲሆን እንተ ለፌኒ ወእንተ ለፌኒ ።

፲፮ ወግብረቶን ግብረተ እግዚእ ፡ ወጽሕፈቶን ጽሕፈተ እግዚአብሔር ውእቱ ፡ ወግሉፋት ላዕለ ጽላት ።

፲፯ ወሰሚዖ ሆሚዐ ቃለ ሕዝብ እንዘ ይጸርሑ ፡ ይቤሎ ለሙሴ ድምፀ ፀብኢት ውስተ ትዕይንት ።

፲፰ ወይቤሎ ሙሴ ኢኮነ ዝንቱ ድምፅ ዘመላእክት እለ ይትኄየሉ ፡ ወኢኮነ ድምፀ መላእክት ዘፀብዐ አላ ድምፀ መልእክቱ ለወይን እሰምዕ አንሰ ።

፲፱ ወሰበ ቀርበ ሙሴ ኀበ ትዕይንት ርእዮ ለውእቱ ላሕም ወተውኔት ወተምዐ ወገደፎን እምውስተ እደዊሁ ለእልክቱ ክልኤ ጽላት ወቀጥቀጦን በታሕተ ደብር ።

፳ ወነሥአ ለውእቱ ላሕም ዘገብሩ ወአውዓዮ በእሳት ወሐረዮ ወአድቀቆ ወዘረዎ ውስተ ማይ ወአስተዮሙ ኪያሁ ለደቂቀ እስራኤል ።

፳፩ ወይቤሎ ሙሴ ለአሮን ምንተ ረሰይከ ዝንተ ሕዝበ ፡ ከመ ታምጽእ ላዕሌሆሙ ኃጢአተ ዓቢየ ።

፳፪ ወይቤሎ አሮን ለሙሴ ኢትትመዓዕ እግዚእ ላዕሌየ ለሊከ ተአምር ግእዞሙ ለእሉ ሕዝብ ።

፳፫ ወሰበ ይቤሉኒ ግበር ለነ አማልክተ እለ የሐውሩ ቅድሜነ እስመ ዝንቱ ሙሴ ዘአውጽአነ እምድረ ግብጽ ኢነአምር ምንተ ኮነ ።

፳፬ ወእቤሎሙ ዘቦ እምኔክሙ ወርቀ አምጽኡ ፡ ወአምጽኡ ወወሀቡኒ ወወረውክዎ ውስተ እሳት ፡ ወወጽአ ዝንቱ ላሕም ።

፳፭ ወሰበ ርእየ ሙሴ ከመ ዓለወ ሕዝብ ፡ እስመ አዕለ ዎሙ አሮን ፡ ወኮኑ ሰሐቀ ለጸላእቶሙ ።

፳፮ ወቆመ ቅድመ ትዕይንት ወይቤ ዘኀረዮ እግዚአብሔር ይምጻእ ኀቤየ ፡ ወተጋብኡ ኀቤሁ ኵሉ ደቂቀ ሌዊ ።

፳፯ ወይቤሎሙ ከመዝ ይቤ እግዚአብሔር አምላከ እስራ ኤል አሐዱ አሐዱ ይፁር ሰይፎ ፡ ወሑሩ ወዕግቱ እምአንቀጽ እስከ አንቀጽ ትዕይንት ፡ ወአሐዱ አሐዱ ይቅትል እኅዋሁ ፡ ወአሐዱ አሐዱ ይቅትል ካልኦ ፡ ወአሐዱ አሐዱ ይቅትል ዘቅሩቦ ።

፳፰ ወገብሩ ደቂቀ ሌዊ በከመ ይቤሎሙ ሙሴ ፡ ወወድቀ እምሕዝብ ይእተ አሚረ ሠላሳ ምእት ብእሲ ።

፳፱ ወይቤሎሙ ሙሴ ፡ አንፈስክምዎ ዮም ለእግዚአብ ሔር በእደዊክሙ አሐዱ አሐዱ እምኔክሙ በወልዱ ወበእኁሁ ከመ ትትወሀብ ለክሙ በረከት ።

፴ ወኮነ በሣኒታ ይቤሎሙ ሙሴ ለሕዝብ ፡ አንትሙ ኀገ ይክሙ ኀጋየ ዓቢየ ፡ ወይእዜኒ አዐርግ ኀበ እግዚአብሔር

ናገራትን የከፋይቱን ነገር ይቅር አለ (ተወ) ።

ሙሴም ተመልሶ ከደብረ ሲና ወረደ ፡ ዐሠርቱ ቃላት የተጻፉበቸው ሁለቱም ጽላቶች በእጁ ተይዘው ነበር ፡ ጽላቶቹም የፊንና ናቸው እንዚህም በጐናቸው በሁለት ወገን ግራና ቀኝ ዐሠርቱ ቃላት የተጻፉበቸው ናቸው ።

አሠራራቸው የጌታ ሥራ ነው ፡ አጻጻፋቸውም የእግዚአብሔር አጻጻፍ ነው ፡ (ዐሠርቱ ቃላትም) በሁለቱ ጽላቶች ላይ ተቀርጸዋል ፡ (ተጽፈዋል) ።

ኢያሱም የሕዝቡን ጩኸት ሰምቶ ሙሴን በከተማው የሰልፍ ድምፅ አለ (እሰማለሁ) አለው ።

ሙሴም ይህ የምትሰማው ለሰልፍ የሚበረታቱ የአርበኞች ድምፅ አይደለም የተሸናፊዎች ድምፅም አይደለም ድምፀ ፋሕሉ ለወይን) እስራኤል ያልፈላ ጥሽ ጠጅ ጠጥተው የሆነውንና ያልሆነውን ይለፈልፋሉ እሰማለሁ እንጂ አለው ። ዘፀ ፴፩ ፲፰ ።

ሙሴም ወደ ከተማው በቀረበ ጊዜ ጥጃውንና ዘፈኑን አይቶ ተቈጣ ፡ እሊህ ሁለቱን ጽላቶች ከእጆቹ ጥሎ ከተራራው በታች ሰበራቸው ።

የሠሩትንም ጣዖት (ጥጃ) ወስዶ በእሳት አቃጠለው ፡ ፈጭቶም አደቀቀው ፡ ከፈሳሽ ውኃም በጥብጦ ለእስራ ኤል ልጆች ያነኑን አጠጣቸው ።

ሙሴም አሮንን በነሱ ላይ ታላቅ ኃጢአት ልታመጣበ ቸው ይህን ሕዝብ ለምን እንዲበድል አደረግኸው አለው።

አሮንም ሙሴን እንዲህ አለው ! አቤቱ በኔ ላይ አት በሳጭብኝ የኒህ ወገኖች ሥራቸውን አንተው ቀሉ ታው ቀዋለህ ።

ከግብጽ አገር ያወጣን ሰው ሙሴ ምን እንደ ሆነ እና ውቅምና በፊት በፊታችን የሚሄዱልን ጠላቶቻችንን የሚ ያጠፉልን አማልክት ሥራልን ቢሉኝ ።

እኔም ከናንተ ወርቅ ያለው አምጡ አልኳቸው እነ ሱም አምጥተው ሰጡኝ እኔም እሳት አስነድጄ በዚያ ላይ ጣልሁት ፡ ይህም ጥጃ ወጣ ።

ሙሴም ኦሮን አስወንጅሏቸዋልና ለጠላቶቻቸውም መዘባበቻ ሁነዋልና ሕዝቡ እንደ ወነጀሉ ፡ በየ ጊዜ እግ ዚአብሔር የወደደው የመረጠው ሰው ወደኔ ይምጣ አለ።

በከተማው መካከል ቆሞ እንዲህ የሌዊም ልጆች ወደሱ ተሰበሰቡ ።

የእስራኤል ፈጣሪ እግዚአብሔር አንዱም አንዱም ሰይፉን በብብቱ ይሸከም ፡ (በወገቡ ይታጠቅ) ከበርም እስ ከ ከተማው በር ሂዱችሁ ክበቡ ፡ አንዱም አንዱም ወንድ ሙን ይግደል ፡ አንዱም አንዱም ባልንጀራውን ይግደል አንዱም አንዱም ጎረቤቱን ይግደለው ብሏል አለ ።

የሌዊም ልጆች ሙሴ እንዳላቸው አደረጉ ፡ ያን ጊዜ ም ከሕዝቡ ሦስት ሺህ ሰው ሞተ ። ፩ ቆሮ ፲ ፯ ።

ሙሴም የእግዚአብሔር በረከቱ ትሰጣችሁ ዘንድ በእ ጆቻችሁ ከናንተ አንዱም አንዱ ልጁን ወንድሙን በመግ ደላችሁ ዛሬ እግዚአብሔርን ደስ አሰኛችሁት አላቸው ።

በበነጋው እንዲህ ሆነ ሙሴ ወገኖቹን ታላቅ በደል በድላችኋል ፡ አሁንም አማልጄ ኃጢአታችሁን አስተሠር

ከመ አስተሥሪ ለክሙ ኃጢአተክሙ ።

፴፩ ወገብአ ሙሴ ኀበ እግዚአብሔር ወይቤ፣ እስእለከ እግዚኦ፣ ናሁ አበሱ እሉ ሕዝብ አበሳ ዓቢየ፣ ወገብሩ ሎሙ አማልክተ ዘወርቅ ።

፴፪ ወይእዜኒ እመ ተኀድግ ሎሙ ዘንተ ኃጢአተ ኅድግ፣ ወእመ አከሰ ደምስስ ኪያየ እመጽሐፍከ ዘጸሐፍከኒ ።

፴፫ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለሙሴ ለዝንቱ ዘአበሰ በቅድሜየ እደመስሶ እመጽሐፍየ ።

፴፬ ወይእዜኒ ሑር ወምርሖሙ ለሕዝብየ ውስተ መካን ዘእቤለከ፣ ወናሁ መልአክየ የሐውር ቅድመ ገጽከ፣ ወአመ ዕለተ እኖሕዮሙ አገብእ ላዕሌሆሙ ኃጢአቶሙ ።

፴፭ ወቀተለ እግዚአብሔር እምሕዝብ በእንተ ዘገብሩ ላሕመ ዘገብረ ሎሙ አሮን ።

ምዕራፍ ፴፫ ።

፩ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለሙሴ ሑር ወዕርግ እምዝየ አንተ ወሕዝብከ ዘአውጻእከ እምድረ ግብጽ፣ ውስተ ምድር ዘመሐልኩ ለአብርሃም ወለይስሐቅ ወለያዕቆብ እንዘ እብል ለዘርእክሙ እሁብ ።

፪ ወእፌንዎ ለመልአክየ ቅድሜከ ወያወጽኦሙ ለከናኔዎን ወለአሞሬዎን፣ ወለኬጤዎን፣ ወለፌርዜዎን፣ ወለጌርጌሴዎን፣ ወለኤዌዎን፣ ወለኢያቡሴዎን ።

፫ ወኢያበውአከ ውስተ ምድር እንተ ትውኅዝ ሐሊበ ወመዓረ፣ ወኢየዓርግ ምስሌከ በእንተ ሕዝብከ እለ ያገዝፉ ክሳዶሙ ከመ ኢያኅልቆሙ በፍኖት ።

፬ ወሰበ ሰምዑ ሕዝብ ዘንተ ነገረ እኩየ ለሀዉ ላሀ ዓቢየ ።

፭ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለሙሴ በሎሙ አንትሙሰ ሕዝብ ዘያገዝፍ ክሳዶ አንትሙ፣ ዑቁ ከልእተ መቅሠፍተ ኢያምጽእ ላዕሌክሙ፣ ወአጠፍአክሙ ወይእዜኒ አሰስሉ አልባሰ ክብርክሙ ወሠርጕክሙ ወአርእየክሙ ዘእሬስየክሙ ።

፮ ወአሰሰሉ ደቂቀ እስራኤል ሠርጓቲሆሙ ወአልባሲሆሙ በደብረ ኮሬብ ።

፯ ወነሥአ ሙሴ ሐይመቶ ወተከለ አፍአ ርኁቀ እምትዕይንት፣ ወተሰምየት ደብተራ ዘመርጡል፣ ወኮነ ኵሉ ዘየኀሥሥ ለእግዚአብሔር የሐውር ኀበ ይእቲ ደብተራ ዘአፍኣ እምትዕይንት ።

፰ ወሰበ የሐውር ሙሴ ይበእ ውስተ ይእቲ ደብተራ ዘአፍኣ እምትዕይንት ይቀውም ኵሉ ሕዝብ ወይኔጽር አሐዱ

ይላችሁ ዘንድ ወደ እግዚአብሔር (ወደ ደብረ ሲና) እወጣለሁ አላቸው ። ፩ ሳሙ፣ ፲፪ ፳ ።

ሙሴም ወደ እግዚአብሔር ተመልሶ አቤቱ እለምንሃለሁ እነሆ እኒህ ሕዝብ ታላቅ በደል በደሉ የወርቅ አማልክትን ለራሳቸው ሠሩ አለ ።

አሁንም ይህን ጽኑ በደል (በቸርነትህ) ይቅር ብትላቸው ይቅር በላቸው ያለዚያ ግን ከጻፍከኝ መጽሐፍህ እኔን ደምስሰኝ ። መዝ፣ ፷፱ ፳፰፣ ሮሜ ፱ ፫ ።

እግዚአብሔርም ሙሴን እንዲህ አለው ፤ በፊቴ የበደለኝን ይህን ወገን ከመጽሐፌ አውጥቼ እደመስሰዋለሁ ። አለው ። ዘሌዋ፣ ፳፫ ፴፣ ሕዝ፣ ፲፰ ፬ ።

አሁንም ሂድ እነዚህን ወገኖች መርተህ ወዳልኩህ ቦታ ውሰዳቸው፣ እነሆም መልአኬ በፊትህ ይሄዳል ነገር ግን (በመዓት) በጐበኘኋቸው ቀን ኃጢአታቸውን በራሳቸው ላይ አመጣባቸዋለሁ ። ዘኍ፣ ፳ ፲፮ ።

አሮን ሠርቶ የሰጣቸውን ላም አምላክ አድርገው ስላመለኩ እግዚአብሔር ከሕዝቡ ወገን ብዙ ሰው ገደለ (አጠፋ)።

ምዕራፍ ፴፫ ።

እግዚአብሔር ሙሴን እንዲህ አለው ፤ ለልጆቻችሁ እሰጣታለሁ ብዬ ለአብርሃም ለይስሐቅ ለያዕቆብ ወደ ማልኩላቸው (ወደ ከነዓን) ከግብጽ አገር ከወጣኻቸው ወገኖችህ ጋር አንተ ከዚህ አገር ወጥተህ ሂድ ።

መልእክተኛዬንም ከንተ አስቀድሜ ወደ ከነዓን እሰዳለሁ፣ እሱም ሂዶ ከናኔዎንን አሞሬዎንን ኬጤዎንን ፌርዜዎንን ጌርጌሴዎንን ኤዌዎንና ኢያቡሴዎንን (ከከነዓን አገር) ያወጣቸዋል (ያጠፋቸዋል)።

እሱም እየመራ ወስዶ ወተትንና ማርን ወደምታፈሰው ምድር አላገባህም፣ እኔ ግን የበደሉኝን በደል (እስቤ) በጐዳና እንዳላጠፋቸው ክሣደ ልቡናቸውን ስላጸኑ ወገኖችህ ከፊት ከንተ ጋር አብሬህ አልወጣም አለው ።

ሕዝቡም ይህን ክፉ ቃል በሰሙ ጊዜ ጽኑ ልቅሶ አለቀሱ ። ፪ ሳሙ፣ ፲፱ ፳፬ ።

እግዚአብሔር ሙሴን የእስራኤልን ልጆች እንዲህ በላቸው አለው እናንተስ ክሣደ ልቡናውን ያጸና ወገኖች ናችሁ፤ ከዚህ ቀድሞ ከመጣሁት መቅሠፍት ሌላ መቅሠፍት አምጥቼ እንዳላጠፋችሁ ዕወቁ ተጠንቀቁ፣ አሁንም ለጣዖቱ በዓል ከብራችሁበት አጊጻችሁበት የዋላችሁበትን ልብስ ከናንተ አስወግዱ ይህን ያደረጋችሁ እንደሆነ የማደርግላችሁን አሳያችኋለሁ ።

የእስራኤልም ልጆች ለጣዖቱ በዓል (ያጌጹበት) ልብሳቸውንና ጌጻቸውን በኮሬብ ተራራ አስወገዱ፣ (አራቁ)።

ሙሴም ድንኳኑ ይዞ ከከተማ በአፍኣ ራቅ አድርጎ ተከላት ይህችውም ደብተራ ኦሪት ተባለች ያን ጊዜ እግዚአብሔርን በሕግ በአምልኮት የሚሻው ሰው ሁሉ ከከተማ በአፍአ ወደ ተተከለች ወደዚያች ድንኳን ይሄድ ነበር ። ዘኍ፣ ፲፯ ፳፯ ።

ሙሴ ከከተማ በአፍኣ ራቅ ብላ ወደ ተተከለች ድንኳን ሊገባ በሄደ ጊዜ ሕዝብ ሁሉ ይቆም ነበር እስኪገባም

አሐዱ ኀበ ኆኅተ ደብተራ፤ ወይሬእይዎ ለሙሴ ሶበ የሐ
ውር እስከ ይበውእ ውስተ ደብተራ ።
፱ ወእምከመ ቦአ ሙሴ ውስተ ደብተራ ይወርድ ዓምድ
ዘደመና እንዘ ይቀውም ኀበ ኆኅተ ደብተራ፤ ወይትናገሮ
እግዚአብሔር ለሙሴ ።
፲ ወይሬእዮ ኵሉ ሕዝብ ለውእቱ ዓምድ ዘደመና እንዘ
ይቀውም ኀበ ኆኅተ ደብተራ ፤ ወይትናገር እግዚአ
ብሔር ምስለ ሙሴ፤ ወቀዊሞሙ ኵሉ ሕዝብ ኀበ ኆኅተ
ደብተራሆሙ ይሰግዱ ።
፲፩ ወይትናገሮ እግዚአብሔር ለሙሴ ገጸ በገጽ ከመ ይት
ናገር ብእሲ ምስለ ዓርኩ፤ ወይገብእ ውስተ ትዕይንት
ወጽሙድስ ሆሴዕ ወልደ ነዌ ወሬዛ ውእቱ ወኢይወጽእ
እምትዕይንት ።
፲፪ ወይቤሎ ሙሴ ለእግዚአብሔር ናሁ ትቤለኒ ስዶ ለዝ
ንቱ ሕዝብ፤ ወበሕቱ ኢነገርከኒ ዘትፌኑ ምስሌየ፤ ወለሊከ
ትቤለኒ ኪያከ አእመርኩ እምኵሉ ፤ ወረከብከ ሞገሰ
በኀቤየ ።
፲፫ ወለእመሰኬ ረከብኩ ሞገሰ በኀቤከ አስተርእየኒ ገሃደ
ሊተ ወአእምር ወእርአይከ ከመ ይኩነኒ ረኪበ ሞገስ
በቅድሜከ ዮም፤ ወከመ አእምር ከመ ሕዝብከ ውእቱ ዝ
ንቱ ሕዝብ ዓቢይ ።
፲፬ ወይቤሎ እግዚአብሔር አነ አሐውር ቅድሜከ ወአዐ
ርፈከ ።
፲፭ ወይቤሎ ሙሴ ለእግዚአብሔር እመ አንተ ለሊከ ኢተ
ሐውር ስሌነ ወኢታወጽአነ እምዝየ፤ በምንት ይትዓ
ወቅ ከመ አኅሁ ረከብኩ ሞገሰ በቅድሜከ አነኒ ወሕዝብ
ከኒ ዘእንበለ ሶበ ሖርከ ምስሌነ ።
፲፮ ወንከብር አነኒ ወሕዝብከኒ በኀበ ኵሉ አሕዛብ ዘሀሎ
ውስተ ኵሉ ምድር ።
፲፯ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለሙሴ ዘንተኒ ነገረ ዘትቤለኒ
እገብር ለከ፤ ወረከብከ ሞገሰ በቅድሜየ ወአአምረከ እም
ኵሉ ።
፲፰ ወይቤሎ ሙሴ ለእግዚአብሔር አርእየኒ ስብሐቲከ ።
፲፱ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለሙሴ አነ አኀልፍ ቅድሜከ
በስብሐትየ ወእጼውዕ ስመ እግዚአብሔር በቅድሜከ ወእ
ምሕሮ ለዘመሐርክዎ፤ ወእሣሀሎ ለዘተሣሀልክዎ ።
፳ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለሙሴ ርእዮተ ገጽየሰ ኢት
ክል እስመ አልቦ ዘይሬኢ ገጽየ ወየሐዩ ።
፳፩ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለሙሴ ናሁ መካን ኀቤየ ሀሎ
ወትቀውም ውስተ ኰኵሕ፤ እስከ የኀልፍ ስብሐትየ ።
፳፪ ወአነብረከ ውስተ ስቍረተ ኰኵሕ ወእከድን እዴየ
በላዕሌከ እስከ አኀልፍ ።
፳፫ ወአሴስል እዴየ ወይእተ ጊዜ ትሬኢ ድኅሬየ፤ ወገጽ
የሰ ኢያስተርኢ ለከ ።

ድረስ በሚሄድበት ጊዜ አንዱም አንዱ በድንኳኑ ደጃፍ
ሁኖ ሙሴን ያየው ነበር ። መዝ፡ ፺፱ ፯ ።
ሙሴም ወደ ድንኳኑ ከገባ በኋላ ዓምደ ደመና ወርዶ
በድንኳኑ ደጃፍ ይቆም ነበር፤ እግዚአብሔርም ሙሴን
ቃል ለቃል ይነጋገረው ነበር ።
ያንንም ዓምደ ደመና በድንኳኑ ላይ ቆሞ ሕዝቡ ሁሉ
ያየው ነበር፤ እግዚአብሔርም ከሙሴ ጋር ቃል ለቃል
ይነጋገር ነበር፤ ሕዝቡም ሁሉ በየድንኳናቸው ቁመው
(ለጌታ) ይሰግዱለት ነበር ። ዘዳግ፡ ፭ ፳፩ ።
እግዚአብሔርም ሙሴን ሰው ከወዳጁ ጋር እንደሚነ
ጋገር ፊት ለፊት ይነጋገረው ነበር፤ (ከተነጋገረውም በኋላ)
ወደ ከተማው ይመለስ ነበር፤ አገልጋዩ የነዌ ልጅ ሆሴዕ
ግን ገና ሕፃን ነበርና ከከተማው አይወጣም ነበር ።
ሙሴም እግዚአብሔርን እነሆ ይህንን ሕዝብ አንተ
መርተህ ውሰደው አልከኝ፤ ነገር ግን አንተ ከኔ ጋር የም
ትልከውን ሰው አልነገርከኝም፤ አንተ ከሁሉ ይልቅ አን
ተን ወደድኩህ፤ በኔ ዘንድ ባለሟልነትን አገኘህ አልከኝ
በንተም ዘንድ ባልሟልነትን ካገኘሁ ፊትህን ገልጠህ አሳ
የኝ፤ ለኔም ዛሬ በንተ ዘንድ ባልሟልነትን ማግኘት ይሆነኝ
ዘንድ ይህም ወገንህ በንተ ዘንድ የከበረ ወገን እንደሆነ ዐ
ውቅ ዘንድ ፊትህን አይህ ዘንድ ገልጠህ አሳየኝ አለው ።
እግዚአብሔርም እኔ በፊትህ እሄዳለሁ አሳርፍህ
ማለሁ አለው ። ዘፀ፡ ፴፬ ፱ ።
ሙሴም እግዚአብሔርን እንዲህ አለው አንተው ራስህ
ከኛ ጋራ ካልሄድክ ከዚህ ቦታም ካላወጣኸን አንተ ከኛ
ጋራ ብትሄድ ነው፤ እኛም በንተ ዘንድ ባልሟልነትን ቁና
ገኝ ነው እንጂ እኔም ሆንኩ ወገኖችህ (እስራኤል) በንተ
ዘንድ ባለሟልነትን እንዳገኘሁ በምን ይታወቅ፤ አለው ።
አንተ ከኛ ጋራ ከሄድክ ግን እኔም ወገኖችህ (እስራ
ኤል) በዚህ ዓለም ላይ ባሉ አሕዛብ ሁሉ ዘንድ እንከብራ
ለን አለው ።
እግዚአብሔርም ሙሴን እንዲህ አለው፤ በኔ ዘንድ
ባለሟልነትን አግኝተኻልና ከሁሉም ለይቼ ወድጄኻለሁና
ያነን ያልከኝን ነገር አደርግልኻለሁ አለው ።
ሙሴም እግዚአብሔርን ጌትነትህን (ገልጠህ) አሳየኝ
አለው ። ኤር፡ ፴፩ ፲፬ ። ሮሜ ፬ ፬፤ ፱ ፲፭ ።
እግዚአብሔር ሙሴን እንዲህ አለው፤ እኔ በፊትህ
የጌትነቴን ስም እየጠራሁ በፊትህ አልፋለሁ የምምረውን
እምረዋለሁ ይቅር የምለውንም ይቅር እለዋለሁ ።
እግዚአብሔርም ሙሴን ፊቴን አይቶ የሚድን የለምና
ፊቴንስ ማየት አትችልም አለው ።
እግዚአብሔር ሙሴን እንዲህ አለው እነሆ በኔ ዘንድ
ቦታ አለ፤ የጌትነቴም ቃል ተነግሮ እስኪፈጸም ድረስ በአ
ለቱ ላይ ትቀመጣለህ ። ኢሳ፡ ፪ ፳፩ ።
በአለቱም ውስጥ አኖርኻለሁ፤ የጌትነቴንም ነገር ተና
ግሬ እስካልፍ ድረስ እጄን በላይህ እጋርዳለሁ (በሥልጣኔ
እሠውርኻለሁ) ።
(በዋሻው ውስጥ ሳለህ) እጄን ካንተ ላይ አነሣለሁ ያን
ጊዜ ኋላዬን ታያለህ፤ ፊቴን ግን አታየውም ዮሐ፡ ፩ ፲፰ ።

ምዕራፍ ፴፬ ።

ምዕራፍ ፴፬ ።

፩ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለሙሴ ቀርጽ ለከ ክልኤተ ጽላ
ተ ዘእብን በከመ ቀዳሚያት ፡ ወዕርግ ኀቤየ ውስተ ደብር
ወእጽሕፍ ውስተ ውእቶን ጽላት ዝከተ ነገረ ዘሀሎ ውስተ
ቀዳሚያት ጽላት ዘቀጥቀጥከን ።

እግዚአብሔር ሙሴን እንዲህ አለው ፤ እንደ ፊተኞቹ
ሁለት የእብን በረድ ጽላቶችን ቀርጸህ ወደ ደብረ ሲና
ወደኔ ውጣ ፡ በሰበርካቸው በቀደሙት ሁለት ጽላቶች
ተጽፎ የነበረውን ያን ዐሠርቱ ቃላትን በነዚያ ጽላቶች ላይ
እጽፋለሁ ። ዘዳግ፡ ፲ ፩ ።

፪ ወኩን ድልወ ለነግህ ፡ ወተዓርግ ውስተ ደብረ ሲና
ወቁም ህየ ላዕለ ርእሰ ደብር ።

ለነገም የተዘጋጀህ ሁን ነገ ይህን ጊዜ እኔ ወዳለሁበት
ወደ ደብረ ሲና ወጥተህ በተራራው ራስ ላይ ቁም ።

፫ ወአልቦ ዘየዓርግ ምስሌከ ፡ ወአልቦ ዘይሄሉ ውስተ
ኵሉ ደብሩ ወአባግዕኒ ወአልሕምትኒ ኢይትረዐዩ ቅሩበ
ለውእቱ ደብር ።

ካንተ ጋር የሚወጣ ሰው የለም (አይኑር) በተራራ
ውም ዙርያ ሁሉ የሚኖር ሰው አይኑር ፡ (እንኳን ሰው)
ላሞችና በጎች ስንኳ በተራራው አቅራቢያ አይሠማሩ
አለው ።

፬ ወወቀረ ሙሴ ክልኤ ጽላተ ዘእብን በከመ ቀዳሚያት ፡
ወነሥአ በእዴሁ እልክተ ክልኤ ጽላተ ዘእብን ፡ ወጌሠ
በጽባሕ ወዓርገ ሙሴ ውስተ ደብረ ሲና ፡ በከመ አዘዞ
እግዚአብሔር ።

ሙሴም እንደ ቀደሙት ሁለት የእብን በረድ ጽላቶች
ቀርጾ እነዚያን ሁለት የእብን በረድ ጽላቶች በእጁ ይዞ
እግዚአብሔር እንዳዘዘው ጧት ተነሥቶ ገስግሶ ወደ
ደብረ ሲና ወጣ ።

፭ ወወረደ እግዚአብሔር በደመና ወቆመ ህየ ወጸውዐ
በስመ እግዚአብሔር ።

እግዚአብሔር በደመና ወርዶ በዚያ (በደብረ ሲና)
ቆመ ፡ ገዥ የሚሆን ስሙንም እግዚአብሔር ብሎ ጠራ ።

፮ ወኀለፈ እግዚአ ቅድመ ገጹ ፡ ወስምየሰ እግዚአ እግ
ዚአብሔር መሐሪ ወመስተሣህል ፡ ርኁቀ መዓት ወብዙኀ
ምሕረት ወጻድቅ ።

ያን ጊዜ ጌታ እግዚአብሔር ስሜ መሐሪ ፡ ይቅር ባይ
ከመዓት የራቀ ፡ ምሕረቱ የበዛ እውነተኛ ነው እያለ
በሙሴ ፊት አለፈ ። ኢዩ፡ ፪ ፲፫ ። ሮሜ ፪ ፬ ።

፯ ዘየዓቅብ ለጽድቅ ወይገብር ምሕረተ ለአእላፍ ወዘያሴ
ስል ዓመፃ ወጌጋየ ወኃጢአተ ፡ ወለመአብስስ ኢያነጽሖ ፡
ዘያገብእ ኃጢአተ አበው ላዕለ ውሉድ ወላዕለ ውሉደ ው
ሉድ እስከ ሣልስ ወራብዕ ትውልድ ።

(እውነትን) የሚጠብቃት እሱ ነው ፡ ለብዙሰዎች ይቅ
ርታን፡ ግፍን በደልን ኃጢአትን ከሰው የሚያርቅ እሱ
ነው ፡ በደለኛውን ግን ከፍዳ አያነጻውም ፡ ያባቶችን ኃጢ
አት በልጆች ፡ የልጆችንም ኃጢአት በልጅ ልጆች ላይ
እስከ ሦስት እስከ አራት ትውልድ ድረስ የሚያመጣ
እሱ ነው ።

፰ ወጐጕአ ሙሴ ወደነነ ውስተ ምድር ወሰገደ ለእግዚ
ብሔር ።

ሙሴም ይህን ሰምቶ ፈጥኖ ወደ ምድር ወድቆ ለእ
ግዚአብሔር ሰገደ ። ኤር፡ ፴፪ ፲፰ ።

፱ ለእመ ረከብኩ ሞገሰ በቅድሜከ ይሑር እግዚእየ
ምስሌየ ፡ እስመ ዝንቱ ሕዝብ ጽኑዐ ክሣድ ውእቱ ፡ ወተ
ሥሃል ኃጣውአ ወአበሳሁ ለሕዝብከ ፡ ወንከውን ለከ ።

ሙሴ እግዚአብሔርን እንዲህ አለው ፤ በፊትህ ባለሟ
ልነትን አግኝቼ እንደሆነ አንተ ጌታዬ ከኔ ጋር ሂድልኝ ፡
ይህ ወገን ከሣደ ልቡናውን ያጸና ነውና ፡ አንተ ግን የዚ
ህ ሕዝብ በደሉን ኃጢአቱን ይቅር በለው ፡ (ይህን) ያደረ
ግህለት እንደሆነ እኛም ላንተ እንሆናለን (እንገዛለን) ።

፲ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለሙሴ ናሁ አነ እሠይም ለከ
ኪዳነ በቅድመ ኵሉ ሕዝብከ ወእገብር ለከ ዓቢያተ ወከ
ቡራተ ዘኢኮነ ከማሁ ውስተ ኵሉ አሕዛብ ወውስተ ኵሉ
ምድር ፡ ወይሬኢ ኵሉ ሕዝብ እለ ውስቴቶሙ ሀሎከ ግ
ብሮ ለእግዚአብሔር ፡ እስመ መድምም ውእቱ ዘአነ እገ
ብር ለከ ።

እግዚአብሔርም ሙሴን እንዲህ አለው ፤ በወገኖችህ
ሁሉ ፊት እነሆ ቃል ኪዳን አደርግልኻለሁ (ብርሃኔን በፊ
ትህ እስልብኻለሁ) በዚህ ዓለም ሁሉ እንደሱ ተደርጎ የማ
ያውቅ በሕዝቡም በአሕዛቡም ዘንድ ተደርጎ የማያውቅ
ታላቅና ድንቅ ተአምራቱን አደርግልኻለሁ ይህም እኔ የማ
ደርግልህ ተአምራት ድንቅ ነውና አንተ ያለህበትም ሕዝ
ብ ሁሉ (የኔን) የእግዚአብሔርን ሥራ ያያል ።

፲፩ ወዐቅ አንተ ብሕቱ ኵሉ ዘአነ እኤዝዘከ ፡ ወናሁ አነ
አወጽኦሙ እምቅድመ ገጽክሙ ለከናኔዎን ወለአሞሬዎን
ወለኬጤዎን ወለፌርዜዎን ወለኤዌዎን ወለኢያቡሴዎን ።

ነገር ግን አንተ እኔ የማዝህን ሁሉ ዕወቅ ፡ እነሆ እኔ
አሞሬዎንን ኬጤዎንን ፌርዜዎንን ጌርጌሴዎንን ኤዌዎን
ንና ኢያቡሴዎንን ከፊታችሁ አውጥቼ እሰዳቸዋለሁ ።

፲፪ ወዐቅ እንከ ርእሰከ ፡ ከመ ኢትትመሐል ምስለ እል
ከቱ ሰብእ እለ ይተርፉ ውስተ ይእቲ ምድር እንተ ውስ
ቴታ ትበውኡ ፡ ከመ ኢይኩን ጌጋየ ላዕሌክሙ ።

እንግዲህም ወዲህ በናንተ ላይ ዕዳ በደል እንዳይሆን
በችሁ ወደ ምትገቡበት ወደዚያች አገር ከሞት ከቀሩ ሰ
ዎች ጋራ እንዳትማማል ራስህን ዕወቅ (ጠብቅ) ።

፲፫ ወምሥዋዒቲሆሙ ንሥቱ ፡ ወምስላቲሆሙ ስብሩ ፡
ወአእዋሞሙ ግዝሙ ፡ ወግልፎ አማልክቲሆሙ አውዕዩ

መሠውያዎቻቸውን አፍርሱ ምስሎቻቸውንም ስበሩ ፡
የሚያመልኩባቸው ዛፎቻቸውን ቍረጡ ፡ (ዓይን እጅ እግ

በእሳት ።

፲፬ ወኢትስግዱ ለካልእ አምላክ ፡ እስመ እግዚአብሔር ቀናኢ ስሙ ፡ ወእግዚአብሔር ቀናኢ ውእቱ ።

፲፭ ዮጊ ትትማሐሉ ምስለ እለ ይነብሩ ውስተ ይእቲ ምድር ወትዜምዉ ድኅረ አማልክቲሆሙ ፡ ወትሠውዑ ለአማልክቲሆሙ ፡ ወይጼውዑከ ወትበልዕ እመሥዋዕቶሙ ።

፲፮ ወትነሥእ እምአዋልዲሆሙ ለደቂቅከ ፡ ወአዋልዲከ ትሁብ ለደቂቆሙ ፡ ወያዜምዋሆሙ ለደቂቅከ ድኅረ አማልክቲሆን ፡ ወይዜምዋ አዋልዲከ ድኅረ አማልክቲሆሙ ።

፲፯ ወአማልክተ ዘስብክ ኢትግበር ለከ ።

፲፰ ወሕገ ናእት ዕቀብ ፡ ሰቡዐ መዋዕለ ብላዕ ናዕተ በከመ አዘዝኩከ በዘመኑ በወርኀ ሚያዝያ ፡ እስመ በወርኀ ሚያዝያ ወጻእከ እምድረ ግብጽ ።

፲፱ ወኵሉ ትበዕት ዘይፈትሕ ማኅፀነ ሊተ ውእቱ ፡ በኵሩ ለላሕም ፡ ወበኵሩ ለበግዕ ፡ ወበኵሩ ለእድግ ።

፳ ወለበኵረ እድግሰ ትቤዝዎ በበግዕ ፡ ወእመሰ ኢቤዘውክሁ ሤጠ ትሁብ ፡ ወኵሎ በኵረ ውሉድከ ትቤዙ ወኢታስተርኢ ቅድሜየ ዕራቀከ ።

፳፩ ሰዱሰ መዋዕለ ትገብር ግብረከ ፡ ወበሳብዕት ዕለት ተዓርፍ ፡ ወታዓርፍ ዘርአ ወዓፂደ ።

፳፪ ወበዓለ ሰንበት ትገብር ሊተ ፡ እመ ይቀድሙ ዓፂደ ሥርናይ ፡ ወበዓለ ምኵራብ ።

፳፫ ሠለስተ ጊዜያተ ማእከለ ዓመት ያስተርኢ ኵሉ ተባዕትከ ቅድመ ታቦተ እግዚአብሔር አምላከ እስራኤል ።

፳፬ ወአመ አወፅአሙ ለአሕዛብ እምቅድመ ገጽከ እሰፍሖን ለአድዋሊከ ፡ ወአልቦ ዘይፈትዋ መኑሂ ለምድርከ ።

፳፭ ወሰበ ተዓርግ ሠለስተ ጊዜያተ በዓመት ታስተርኢ ቅድመ እግዚአብሔር አምላክከ ኢትዝባሕ ላዕለ ደም ብኁዕ መሥዋዕትየ ።

፳፮ ወኢይቢት ለነግህ መሥዋዕተ በዓል ዘፋሲካ ።

፳፯ ቀዳሜ እክለ ምድርከ ትወስድ ቤተ እግዚአብሔር አምላክከ ፡ ወኢታብስል በግዐ በሐሊበ እሙ (እንዘ ይጠቡ ሐሊበ እሙ) ።

፳፰ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለሙሴ ጸሐፍ ለከ ዘንተ ነገረ እስመ በዝንቱ ነገር አቀውም ኪዳነ ለከ ወለእስራኤል ።

፳፱ ወነበረ ሙሴ ቅድመ እግዚአብሔር አርብዐ መዓልተ ወአርብዓ ሌሊተ ኢበልዐ እክለ ፡ ወኢሰትየ ማየ ፡ ወጸሐፈ እግዚአብሔር ውስተ ጽላት ዘንተ ነገረ ዐሠርተ ቃላተ ።

ር) የተቀረጹባቸው ጣዖቶቻቸውን በእሳት አቃጥሉ ።

የእግዚአብሔር ስሙ ቀናተኛ ስለሆነ እግዚአብሔርም ለአምላክነቱ ቀናተኛ ነውና ለሌላ አምላክ አትስገዱ ። ዘዐ ፡ ፳ ፭ ፡ ኢሳ ፡ ፶፯ ፲፭ ።

በዚያች ምድር ከሚኖሩ ሰዎች ጋራ እኮ ትማማሉ ይሆናል ፡ አማልክቶቻቸውን ተከትላችሁ በጣዖት አስከትሰስኑ ለጣዖቶቻቸውም ትሠዉላቸው ይሆናል ፡ ወይም እኮ ለጣዖቱ በዓል ይጠሩህና ሄደህ ተረፈ ጣዖቱን ትበላ ይሆናል ። ፩ ቆሮ፡ ፰ ፬ ፡ ፲ ፴፯ ።

ሄደህም ሴቶች ልጆቻቸውን አጭተህ ለወንዶች ልጆችህ ሴቶች ልጆችህን ወስደህ ለወንዶች ልጆቻቸው ታጋባለህ ፡ ያገቡዋቸውም የአሕዛብ ሴቶች ጣዖቶቻቸውን ተከትለው እንዲሰስኑ ያደርጓቸዋል ሴቶች ልጆችህም ጣዖቶቻቸውን ተከትለው እንዲሰስኑ ያደርጓቸዋል (እንዳያደርጓቸው ተጠንቀቅ)። ዘኍ፡ ፳፭ ፩ ፡ ዕዝ፡ ፱ ፪ ።

ተመትተው የተሠሩትን ጣዖቶች ላንተ አታድርግ ፡ (ሠርተህ አታምልክ) ። ዘዐ፡ ፳፫ ፲፭ ።

ቂጣ የምትበሉበት የበዓሉን ሕግ ጠብቅ ፡ ከግብጽ አገር በሚያዝያ ወር ወጥተኻልና በሚያዝያ ወር በዘመኑ ሥርዓቱን ጠብቅ ብዬ እንዳዘዝኩህ ሰባት ቀን ቂጣ ብላ ።

መጀመሪያ የተወለደ ወንድ ወንዱ በኵር ልጅም ለኔ ነው ፡ የላሙም የበጉም የአህያውም በኵር የኔ ነው ።

የአህያውን በኵር ግን በበግ ለውጠው ፡ በበግ ካልለወጥከውም ሽጠህ ዋጋውን ስጥ ፡ የበኵር ልጅህንም ሁሉ ዋጋውን ሰጥተህ ተበዥተህ አስቀረው በፊቴም ባዶ እጅህ አትታይ ፡ (መባእህን ይዘህ ግባ) ።

ስድስት ቀን አረስ ቈፍር ፡ በሰባተኛው ቀን ግን ዕረፍ ፡ ከመዝራትም ከማጨድም ዕረፍ ።

(ሰዎች) አስቀድመው ሥንዴውን በሚያጭዱበት ወራት በሱባዔ በሚከብር በዓል እሸት ነዶውን ይዘህ መጥተህ ለኔ በዓል አድርግልኝ ፡ በዓለ መጸለትንም አድርግልኝ።

ወንድ ወንዱ ሁሉ ለገቢረ በዓል እየወጣ በ፳ኤል ፈጣሪ በእግዚአብሔር ማደርያ ፊት በዓመት ሦስት ጊዜ ያክብር።

አሕዛብን ከፊትህ አስወጥቼ በሰደድኳቸው ጊዜ አውራጃዎችህን አሰፋቸዋለሁ ፡ አገርህንም የሚመኛት ማንም ማን የለም ።

በፈጣሪህ በእግዚአብሔር ፊት ለመታየት በዓመት ሦስት ጊዜ ስትወጣ መሥዋዕቴን በእደረ ደም አትሠዋ ።

የፋሲካው በዓል መሥዋዕትም ለነገ አይደር ።

መጀመሪያ ከእርሻህ የተገኘውን እኽል ወደ ፈጣሪህ ወደ እግዚአብሔር ቤት ውሰድ ፡ በጉንም በናቱ ቅቤ አትቀቅል ። ዘዳግ፡ ፳ ፪ ።

እግዚአብሔርም ሙሴን በዚህ ነገር ለአንተና ለእስራኤል ቃል ኪዳኔን አጸናለሁና ይህንን ነገር ጻፍ አለው ።

ሙሴም አርባ ቀን ፡ አርባ ሌሊት (በደብረ ሲና) ከእግዚአብሔር ጋር ኖረ ፡ እንጀራንም አልበላም ፡ ውኃንም አልጠጣም ፡ እግዚአብሔር ቀድሞ በሁለቱ ጽላቶች ተጽ

፳፱ ወሶበ ወረደ ሙሴ እምደብረ ሲና ወሀለዋ ክልኤቲ ጽላት ውስተ እደዊሁ፣ ወእንዘ ይወርድ እምደብረ ኢያእመረ ከመ ተሰብሐ ኅብረ ገጹ፡ እንዘ ይትናገር ምስለ እግዚአብሔር ።

፴ ወሶበ ርእይዎ አሮን ወኵሉ ደቂቀ እስራኤል ለሙሴ ከመ ተሰብሐ ርእየተ ኅብረ ገጹ ፈርሁ ቀሪቦቶ ።

፴፩ ወጸውዖሙ ሙሴ ወገብኡ ኀቤሁ አሮን ወኵሉ መኳንንተ ትዕይንት ወተናገሮሙ ሙሴ ።

፴፪ ወእምድኅረ ዝንቱ ቀርቡ ኀቤሁ ኵሉ ደቂቀ እስራኤል ወአዘዞሙ ኵሉ ዘተናገሮ ለእግዚአብሔር በደብረ ሲና ።

፴፫ ወሶበ አኅለቀ ተናግሮቶሙ ወደየ ላዕለ ገጹ ግልባቤ በዘይሤውር ገጾ ።

፴፬ ወሶበ የሐውር ሙሴ ቅድመ እግዚአብሔር ከመ ይትናገሮ ያሴስል ግልባቤሁ እስከ ይወጽእ ፣ ወእምከመ ወጽአ ይነግሮሙ ለደቂቀ እስራኤል ኵሉ ዘአዘዞ እግዚአብሔር ።

፴፭ ወርእዩ ደቂቀ እስራኤል ከመ ተሰብሐ ገጹ ለሙሴ ወከመ ወደየ ግልባቤ በዘይሤውር ገጾ እንዘ ይወጽእ ከመ ይትናገሮሙ ።

ምዕራፍ ፴፭ ።

፩ ወአስተጋብአሙ ሙሴ ለኵሉ ማኅበረ ደቂቀ እስራኤል ወይቤሎሙ፣ ዝንቱ ውእቱ ነገር ዘይቤ እግዚአብሔር ከመ ትግበርዎ ።

፪ ሰዱስ መዋዕለ ትገብሩ ግብረክሙ ወበሳብዕት ዕለት ታዕርፉ ቅድስት ሰንበት፣ ዕረፍት ለእግዚአብሔር፣ ኵሉ ዘይገብር በቲ ግብረ ለይሙት ።

፫ ወኢታንድዱ እሳተ በውስተ ኵሉ ማኅደርክሙ በዕለተ ሰንበትየ ።

፬ ወይቤሎሙ ሙሴ ለኵሉ ማኅበረ ደቂቀ እስራኤል እንዘ ይብል ዝንቱ ውእቱ ቃል ዘአዘዘ እግዚአብሔር እንዘ ይብል ።

፭ ንሥኡ እምኔክሙ መባአ ለእግዚአብሔር ኵሉ ዘሐለየ ልበሙ ያምጽኡ እምቀዳሚ ንዋዮሙ እምወርቅ ወእምብሩር ወእምብርት ።

፮ ወያክንት ወኅብረ ከብድ፣ ወለይ ክዑብ፣ ወቢሶስ ፍቱል፣ ወፀጕረ ጠሊ ።

፯ ወማእሰ በግዕ ግቡረ መሐን፣ ወመሐነ መጸጺት ወዕፀ ዘኢይነቅዝ ።

፰ ወቅብሀ ለማኅቶት፣ ወአፈዋተ ለተቀብዖ፣ ወዕጣናተ ለማዕጠንት ።

፱ ወአእባነ መረግድ፣ ወአእባነ ዘይትኄረው ለኤፉድ ወለሎግዮ ።

፲ ወኵሉሙ ጠቢባነ ልብ ዘውስቴትክሙ ይምጽኡ ወይግበሩ ኵሎ ዘአዘዘ እግዚአብሔር ።

፲፩ ደብተራ፣ ወሠቃቲሃ፣ ወመክደና ወናፃፂቲሃ፣ ወአዕ

ፊው የነበሩ ዐሠርቱ ቃላትን ጻግመኛ በሁለቱ ጽላቶች ጻፈ፣ (በግብር አምላካዊ ጻፈለት) ።

ሙሴም ከደብረ ሲና በወረደ ጊዜ ሁለቱ ጽላቶች በእጆቹ ተይዘው ነበር፣ ከደብረ ሲናም ሲወርድ በደብረ ሲና ከእግዚአብሔር ጋር ሲነጋገር በፊቱ ብርሃን እንደ ተሣለበት አላወቀም ነበር ። ዘፀ፣ ፴፪ ፲፭ ።

አሮንና የሸልም ልጆች ሁሉ ሙሴን በፊቱ ኅብረ መልክዕ ብርሃን ተሥሎበት በዩት ጊዜ ወደሱ መቅረቡን ፈሩ።

ሙሴም ጠራቸው፣ አሮንና የከተማው መኳንንትም ሁሉ ወደሱ ተመለሱ፣ ሙሴም ተነጋገራቸው ።

ከዚህም በኋላ የእስራኤል ልጆች ሁሉ ወደርሱ ቀረቡ እግዚአብሔር በደብረ ሲና የተነጋገረውን ሁሉ (አድርጉ-ብሎ) አዘዛቸው ። ዘፀ፣ ፳፬ ፫ ።

ይህንም ነግሯቸው ከጨረሰ በኋላ ፊቱን የሚሠውርበትን መሸፈኛ በፊቱ ላይ አደረገ። ፪ ቆሮ፣ ፫ ፲፫ ።

ሙሴ እግዚአብሔርን ሊነጋገረው በሄደ ጊዜ ከደብረ ሲና እስኪወጣ ድረስ (መሸፈኛውን) ከራሱ ላይ ያወርድ ነበር፣ ከወጣም በኋላ እግዚአብሔር ያዘዘውን ሁሉ ለእስራኤል ልጆች ይነግራቸው ነበር።

የእስራኤልም ልጆች የሙሴ ፊቱ እንደበራ ሊነግራቸውም (ከደብረ ሲና) ሲወጣ ፊቱም በሚሠውርበት መሸፈኛ እንደሠወረ አዩ።

ምዕራፍ ፴፭ ።

ሙሴ የእስራኤልን ልጆች ማኅበር ሁሉ ሰብስቦ ልታደርጉት እግዚአብሔር የተናገረው ነገር ይህ ነው አላቸው።

ስድስቱን ቀን ሥራችሁን ሥሩበት፣ በሰባተኛው ቅዳሜ ቀን ግን ታርፉ ዘንድ ለእግዚአብሔር የተቀደሰች የዕረፍት በዓል ናት ሥራን የሚሠራበት ሁሉ ይሙት።

ቅዳሜ ቀን በየቤታችሁ ሁሉ (ዕንጨት ሰብራችሁ ፈልጣችሁ) እሳት አታንድዱ ። ዘፀ፣ ፲፮ ፳፫ ።

ሙሴ የእስራኤልን ልጆች ወገኖች ሁሉ እንዲህ ሲል ነገራቸው፣ እግዚአብሔር አድርጉት ብሎ ያዘዘው ቃል ይህ ነው ። ዘፀ፣ ፳፭ ፩-፪።

እናንተ ለእግዚአብሔር የሚቀርብ መባን ከነሱ ተቀበሉ፣ እነሱ ከደገኛው ገንዘባቸው ልቡናቸው ያሰበውን ሁሉ ከወርቅም ከብርም ከናስም ያምጡ ።

ሰማያዊም ሐምራዊም ቀይ ግምጃም ጥሩ በፍታም የፍየል ጠጕር ።

ቀለም የገባ የበግ ቈርበት (በሕረ ግረብ) ሰማያዊ ቈርበት የማይነቅዝም ዕንጨት ።

ዘይትም ለመብራት፣ ሽቱም ለመቀበት ለጣፋጭ ዕጣን ቅመም ።

የመረግድ ዕንቆች ለኤፉድና ለደረት ኪስ የሚሆን የተበሳ እብነ በረድ (ፈርጥ) ያምጡ።

ከናንተም ዘንድ ያሉ በልባቸው ብልሃተኞች የሆኑ ሁሉ መጥተው እግዚአብሔር ያዘዘውን ሁሉ ያድርጉ ።

ማደሪያው ድንኳኑን ማልበሻውን መክደኛውን መያ

| | | |
|---|---|---|
| ማዲሃ፣ ወመናሥግቲሆን ። | | ገሮቹን ምሰሶዎቹን መወርወሪያዎቹን ። |
| ወታቦተ ዘመርጡል፣ ወመፃውሪሃ፣ ወተድባበ ወመንጦላዕተ ዘምሥዋር ። | ፲፪ | ታቦቱን መሎጊያዎቹን የሥርየት መክደኛውን የሚጋርደው መጋረጃውን ። ዘፀ፡ ፵ ፪፣ ዕብ፡ ፱ ፪ ። |
| ወአዕማዲሃ፣ ወምዕማዲሆን፣ ወማእደ፣ ወመፃውርቲሁ፣ | ፲፫ | አዕማዶቹን ምዕማዶቹን ገበታውን መሸከሚያዎቹን። |
| ወኵሎ ንዋያቲሁ፣ ወተቅዋመ ማኀቶት ። | ፲፬ | ዕቃውን ሁሉ መብራት የሚያበሩበት መቅረዙን ። |
| ወኵሎ ንዋያ፣ ወመኀትዊሃ፣ ወቅብዐ ማኀቶት ። | ፲፭ | ዕቃውን ሁሉ ቀንዲሎቹን የመብራቱንም ዘይት ። |
| ወምሥዋዐ ዘዕጣን፣ ወመፃውርቲሁ፣ ወቅብዐ ዘይት ቀብዖ፣ ወዕጣነ ዘየዓጥኑ፣ ወመክደኒ ኆኅት ዘደብተራ ። | ፲፮ | የዕጣኑን መሠውያ (ጽንሐሕ) መሎጊያዎቹን የሚቀቡትንም ዘይት የሚያጥኑትን ዕጣንም ለደብተራ ኦሪት ደጃፍ የሚሆን መጋረጃ ። ዘፀ፡ ፴ ፳፫ ። |
| ወምሥዋዐ ዘመሥዋዕት፣ ወሰቅሰቀ ዘብርት፣ ዘሎቱ መፃውርቲሁ፣ ወኵሎን ንዋያቲሁ፣ ወማእከከ ንዋያቲሁ፣ ወማእከከ ምስለ መንበሩ ። | ፲፯ | ለሚቃጠል መሥዋዕት የሚሆን መሠውያውን የናሱንም መከታ መሸከሚያዎቹን ዕቃዎቹን ሁሉ የመታጠቢያው ሰኑን ዳካውን ከነ መቀመጫው ። |
| ወመንጦላዕተ ዓፀድ፣ ወአዕማዲሁ፣ ወምዕማዲሆን፣ ወመክደኒ አንቀጸ ዓፀድ መታክሊሁ ለደብተራ፣ ወመታክለ ዓፀድ፣ ወአውታሪሆን ። | ፲፰ | የአደባባዩን መጋረጃ ምሰሶዎቹን እግሮቹንም የአደባባዩን ደጃፍ መጋረጃ የድንኳን ካስማዎች የአደባባዩን ካስማዎችና አውታሮቹንም ። |
| ወአልባሲሁ ለአሮን ካህን፣ ወአልባሰ ደቂቁ ዘክህነቶሙ፣ ወአልባሰ በዘይገብሩ በውስተ መቅደስ ። | ፲፱ | በመቅደስ ውስጥ ለማገልገል በብልሃት የተሠሩም የካህኑ የአሮን ልብሶችን በክህነት ለማገልገል የተቀደሱ የልጆቹንም ልብሶች ። ዘፀ፡ ፴፩ ፲ ። |
| ወወፅኡ ኵሉ ማኅበሮሙ ለደቂቀ እስራኤል እምኅበ ሙሴ ። | ፳ | የእስራኤል ልጆች ማኅበሮችም ሁሉ ከሙሴ ፊት ወጡ ። |
| ወአምጽአ አሐዱ አሐዱ በከመ ሐለየ በልቡ፣ ወበከመ ፈቀደ በነፍሱ አምጽአ መባአ ለእግዚአብሔር ለኵሉ ግብረ ደብተራ ዘመርጡል፣ ወለኵሉ መፍቅዳ፣ ወለኵሉ አልባስ ዘመቅደስ ። | ፳፩ | አንዱ አንዱም ልቡ እንዳሰበውና መንፈሱም እንደ ወደደው ለእግዚአብሔር መባውን አመጣ፣ ለመገናኛው ድንኳን ሥራ ሁሉ ለሚያስፈልገው ሁሉ ለመቅደስም ልብሶች ሁሉ ። ዘፀ፡ ፴፱ ፩-፵፩፣ ዘኍ፡ ፬ ፫-፯ ። |
| ወአምጽኡ እደው ዘእምኀበ አንስትኒ ዘከመ ፈቀደ ልበን ማኅተማተ ወአውጻበ፣ ወኀልቀታተ፣ ወሐብላታተ ወአውቃፈ፣ ወኵሎ ሠርጐ ዘወርቅ ። | ፳፪ | ወንዶችም ከሴቶች ዘንድ ልቡናቸው ያሰበውን ማርዳዎችን ንሮ መንደልቆን (ሎቲዎች) ቀለበቶችን ድሪዎችን አምባሮችን የወርቅ ጌጦችንም ሁሉ አመጡ ። |
| ወኵሎ አምጽኡ ወርቀ መባአ ለእግዚአብሔር፣ ወኵሎ ብእሲ ዘረከበ ያክንተ፣ ወኅብረ ከብድ፣ ወለየ ክዑበ ወቢሦሰ ክዑበ፣ ወፀጕረ ጠሊ፣ ወማእሰ በግዕ ግቡረ መሐን፣ ወማእሰኒ ዘሥርየቱ ኅብረ ያክንት ። | ፳፫ | ሁሉም የወርቅን ስጦታ ሁሉ ለእግዚአብሔር አቀረቡ፣ ሰማያዊ ሐርን ሐምራዊ ሐርን ቀይ ግምጃን ዕጽፍ ሁኖ የተፈተለ ቢጫ ሐርን የፍየል ፀጕርም የበሕር ዓረብም ሰማያዊ ኅብረ ቀለም የገባ ብሕረ ዓረብም (የአስቆጣ ቄርበት) አመጡ ። |
| ወአብአ ኵሉ ዘበጽዐ ብጽዐተ፣ ብሩረ ወብርተ መባአ ለእግዚአብሔር ወእምኅበ ተረክበ ዕፀ ዘኢይነቅዝ ለኵሉ ምግባረ መፍቅዳ ለደብተራ አምጽኡ ። | ፳፬ | ስለት የተሳለ ሁሉ የብርን የነሐስን ስጦታ ሁሉ ለእግዚአብሔር መባ አድርጎ አቀረበ፣ የማይነቅዝ ዕንጨት ከተገኘ ዘንድ ለደብተራ ኦሪት ማገልገያ የሚያስፈልገውን ሁሉ አመጡ ። ፩ ዜና መዋ፡ ፳፱ ፰ ። |
| ወብእሲትኒ እንተ ትክል ፈቲለ በእደዊሃ አምጽአት ፈትለ ዘያክንት፣ ወኅብረ ከብድ፣ ወለይ፣ ወቢሦስ። | ፳፭ | በእጅዋ መፍተልን የምትችል ሴትም የሰማያዊውን የሐምራዊውን የቀይና የብጫውን ሐር ፈትል አመጣች። |
| ወኵሎን አንስት እለ ሐለያ በልበን፣ ወበጥበብ ፈተላሁ ለፀጕረ ጠሊ ። | ፳፮ | (እንስጥ ብለው) በልቡናቸው ያሰቡ ሴቶችም ሁሉ አመጡ፣ የፍየሉንም ጠጕር በብልሀነት በጥበብ ፈትሉት፤ |
| ወመላእክትኒ አምጽኡ አእባነ መረግድ፣ ወአእባነ ዘይትኄረው ለኤፉድ ዘላዕለ መትከፍት ወለሎግዮ ። | ፳፯ | አለቆችም የዕንቍ ደንጊያዎች (እብነ በረድ) ለኤፉድና ለደረት ኪስ የሚገቡት ፈርጦችን ። |
| ወቅብዐ ማኅቶት፣ ወቅብዐ ዘይትቀብዖ፣ ወዕጣነ ዘየዓጥኑ ። | ፳፰ | ለመብራት ዘይትን ለቅብዐት ሽቱን ለሚያጥኑት ማዓጭ ዕጣንን አመጡ ። ፩ ዜና መዋ፡ ፳፱ ፮ ። |
| ወኵሉ ብእሲ ወብእሲት ዘፈቀደ ልበሙ ከመ ያብኡ ወይግበሩ ኵሎ ግብረ ዘአዘዘ እግዚአብሔር ለሙሴ አምጽኡ ደቂቀ እስራኤል መባአ ለእግዚአብሔር ። | ፳፱ | ወንዶችና ሴቶች ሁሉ ልቡናቸው የፈቀደውንና እግዚአብሔር በሙሴ ቃል ያዘዘውን ሥራ ሁሉ ይሠሩ ዘንድ የእስራኤል ልጆች ለእግዚአብሔር ስጦታን አመጡ። |
| ወይቤሎሙ ሙሴ ለደቂቀ እስራኤል ናሁ ጸውዖ እግዚአብሔር በስሙ ለበስልኤል ወልደ ኡሬ ወልደ ሖር | ፴ | ሙሴም የእስራኤልን ልጆች እነሆ እግዚአብሔር ከይሁዳ ነገድ የሆነውን የሖር የልጅ ልጅ የኡሬ ልጅ በስል |

| | | |
|---|---|---|
| ዘእምነገደ ይሁዳ ። | | ኤልን በስሙ ጠራው አላቸው ። ፩ ዜና መዋ፡ ፳፪ ፱ ። |
| ወመልአ መንፈሰ እግዚአብሔር፣ ወጥበበ፣ ወልቡና፣ ወአእምሮ፣ ከመ ይኩን ሊቀ ላዕለ ኵሉ ጸረብት ። | ፴፩ | በሥራ ሁሉ በጥበብም በማስተዋልም በዕውቀትም የእናጢዎች ሁሉ አለቃ ይሆን ዘንድ የእግዚአብሔርን መንፈስ ተመላ ። ዘፀ፡ ፴፩ ፪ ። |
| ወይግበር ኵሎ ምግባረ፣ ወይግበር ወርቀ ወብሩረ ወብርተ ። | ፴፪ | ሥራውን ሁሉ ይሠራ ዘንድ በወርቅ በብርና በናስም ይሠራ ዘንድ ። ዘፍ፡ ፵፩ ፴፰፣ ኢዮብ ፴፪ ፰ ። |
| ወይግበር ኪነ ዕንቍ ወዕፀ፣ ወይግበር ኵሎ ግብረ በጥበብ ወይምሀር ። | ፴፫ | በፈርጥ የሚሆነውን የዕንቍ ድንጋይ ይቀርፅ ዘንድ ዕንጨቱንም ይጠርብ ዘንድ በብልሃት የሚሠራውን ሥራ ሁሉ ይሠራ ዘንድና ያስተምርም ዘንድ ። |
| ወወደየ ውስተ ልቡ ሎቱ ወለኤልያብ ወልደ አክሴምክ ዘእምነገደ ዳን ። | ፴፬ | እርሱና የነገደ ዳን የሆነው የአክሴምክ ልጅ ኤልያብን ያስተምሩ ዘንድ በልቡናቸው አሳደረባቸው ። |
| ወመልአሙ ጥበበ ልብ፣ ከመ ያእምሩ ገቢረ ኵሎ ምግባረ መቅደስ፣ ዘይትአነም ከመ ይእንሙ በያክንት፣ ወበኅብረ ክብድ፣ ወበለይ ክዑብ፣ ወቢሦስ ወከመ ይግበሩ ኵሎ ግብረ ጽርበት ዘዘዚአሁ ። | ፴፭ | የመቅደስን ሥራ ሁሉ መሥራትን ይሠሩ ዘንድ በሰማያዊ ሐር በሐምራዊ ሐር ዕጽፍ ሁኖ በተፈተለ ቀይ ሐር በብጫው ሐር የሚሠራውን ሥራ ሁሉ ያውቁ ዘንድ ልዩ ልዩ የአጠራረብም ሥራ ሁሉ ይሠሩ ዘንድ የማስተዋል ጥበብን መላባቸው ። |
| **ምዕራፍ ፴፮ ።** | | **ምዕራፍ ፴፮ ።** |
| ወገብሩ ባስልኤል ወኤልያብ፣ ወኵሎሙ ጠቢባነ ልብ እለ ተውህበ ሎሙ ጥበብ ወአእምሮ፣ ከመ ይግበሩ ኵሎ ግብረ መቅደስ ዘይትፈቀድ፣ ኵሎ ዘአዘዘ እግዚአብሔር ለሙሴ ። | ፩ | የሚፈለገውን ለመቅደስ ማገልገያ ሥራ እንዲሠሩ ጥበብና ዕውቀት የተሰጣቸው ባስልኤልና ኤልያብ የልብ ዕውቀት ያላቸውም ሁሉ እግዚአብሔር በሙሴ ቃል ያዘዘውን ሁሉ ሠሩ ። ዘፀ፡ ፳፰ ፫፣ ኢሳ፡ ፳፰ ፳፮ ። |
| ወጸውዖሙ ሙሴ ለባስልኤል ወለኤልያብ ወለኵሎሙ እለ በሙ ጥበብ ዘወሀበሙ እግዚአብሔር አእምሮ ውስተ ልበሙ ወለኵሎሙ እለ በፈቃደ ልበሙ ይገብሩ፡ ከመ ይግበሩ ወከመ ይሑሩ ውስተ ዝንቱ ግብር ከመ ይፈጽምዎ ። | ፪ | ሙሴም ባስልኤልና ኤልያብን እግዚአብሔር በልባቸው ጥበብን ዕውቀትን የሰጣቸው ሁሉ ሥራውን ለመሥራት በልቡናቸው ፈቃድ የተነሣሡትን ሁሉ ሥራውን ሠርተው ይፈጽሙ ዘንድ ጠራቸው ። |
| ወነሥኡ እምቅድመ ሙሴ መባአ ዘአብኡ ደቂቀ እስራኤል ለኵሉ ምግባረ መቅደስ ከመ ይግበሩ፣ ወእሙንቱሂ ይትዌከፉ ዓዲ ዘያበውኡ እምኀበ እለ ያመጽኡ ነግሀ ነግሀ ። | ፫ | የእስራኤል ልጆች ይሠሩ ዘንድ ለመቅደስ ሥራ ያመጡትን ስጦታ ሁሉ ከሙሴ ፊት ተቀበሉ፣ እነሱም በፈቃዳቸው ያቀረቡትን ዕለት ዕለት ወደርሱ ያመጡ ነበር ። |
| ወመጽኡ ኵሎሙ ጠቢባን እለ ይገብሩ ግብረ መቅደስ አሐዱ አሐዱ በበምግባሪሁ ዘይገብር፣ ይቤልዎ ለሙሴ ብዙኅ መባእ ዘያበውኡ ሕዝብ እምግብር ዘአዘዘ እግዚአብሔር ከመ ይትገበር ። | ፬ | የመቅደሱንም ሥራ የሚሠሩ ጠቢባን ሁሉ አንዱም አንዱም እንደየሥራው በመሥራት መጥተው፣ እግዚአብሔር ይደረግ ዘንድ ካዘዘው ሥራ እጅግ የበዛ ስጦታ ሕዝቡ አመጡ ብለው ለሙሴ ነገሩት ። |
| ወአዘዘ ሙሴ ወሰበከ ውስተ ትዕይንት ለእድ ወለአንስት ወይቤ እምይእዜ ኢይግበሩ መባአ ዘመቅደስ ። | ፭ | ሙሴም ወንድም ሴት ለመቅደስ ስጦታ ከዚህ የበለጠ የሚያመጣ አይኑር ብሎ በሰፈሩ አዘዘ፣ (አወጀም) ። |
| ወተከልአ ሕዝብ እምአብኦ፣ እስመ አከሎሙ ለምግባር ዘይገብሩ፣ ወተርፎሙ ። | ፮ | ሕዝቡም ስጦታን ከማቅረብ ተከለከለ፣ ያመጡት ነገር ሥራን ለመፈጸም በቅቶ ተርፎአቸዋልና ። |
| ወገብሩ ኵሎሙ ጠቢባነ ልብ፣ ምግባረ ደብተራ ዐሠርተ አዕፃደ እምቢሦስ ክዑብ፣ ወእምያክንት ወኅብረ ክብድ፣ ወለይ ክዑብ፣ ወኪሩቤነ ገብሩ በምግባረ ምእናም ። | ፯ | በልባቸው ብልሃተኞች የሆኑ ሁሉ የድንኳኑን ሥራ ከተፈተለ ከጥሩ በፍታ ከሰማያዊና ከሐምራዊ ሐር ከቀይ ግምጃም ዓሥር መጋረጃዎችን ሠሩ፣ ከእነርሱም በላይ ብልህ ሠራተኛ በሚሠራው አሠራር ኪሩቤልን አደረጉባቸው ። ዘፀ፡ ፳፮ ፩፣ ምሳ፡ ፲ ፳ ። |
| ወኑኁ ለአሐዱ ዓፀድ ዕሥራ ወሰመንቱ በእመት፣ ወርኅቡ ርብዕ በእመት ለአሐዱ ዓፀድ፣ በመስፈርቱ ከማሁ ለኵሎሙ አዕፃድ ። | ፰ | ያንዱም መጋረጃ ርዝመት ሃያ ስምንት ክንድ፣ ወርዱም አራት ክንድ ለአንዱ መጋረጃ ነው፣ የመጋረጃዎቹም ሁሉ እንዲሁ በዚያው ልክ ነው ። |
| ወኀምስተ አዕፃደ አስተሳመኩ በበይናቲሆሙ አሐደ ምስለ ካልኡ፣ ወኀምስተ አዕፃደ አስተሳመኩ በበይናቲሆሙ ። | ፱ | አምስቱንም መጋረጃዎች አንዱን ከንዱ ጋር እርስ በርሳቸው አጋጠሙ፣ ደግሞም አምስቱ መጋረጃዎች እንዲሁ አንዱን ከንዱ ጋር አገናኙ ። |

| | | |
|---|---|---|
| ወገብሩ ኀምስ መማስጠ ዘያክንት ላዕለ ክንፈረ አሐዱ ዓፀድ፣ እምጽንፉ በዘየኃብር፣ ወከማሁ ኀምስ መማስጠ ገብሩ በክንፈረ ዓፀድ ካልእ በዘየኃብሩ ። | ፲ | በአንዱ መጋረጃ ክፈፍ ላይ ከሰማያዊ ሐር አምስ ቀለበቶችን ከመጋረጃው ጫፍ እንዲጋጠሙ አደረጉ፤ እንዲሁም በሁለተኛው መጋረጃ ክፈፍ አምስ ቀለበቶች እንዲጋጠሙ አደረጉ ። |
| ወገብሩ ኀምስ ሞፃዳተ ዘወርቅ ወአኀበሩ አዕፃዳተ አሐደ ምስለ ካልኡ በሞፃዳት፣ ወኮነ ደብተራሁ አሐደ ። | ፲፩ | አምስ የወርቅ መያዣዎችን ሠሩ፤ መጋረጃዎቹንም እርስ በርሳቸው በመያዣዎች አያያዙዋቸው ድንኳኑም አንድ ሆነ ። |
| ወገብሩ ዐሥርተ ወአሐደ አዕፃደ ዘሠቅ ዘይሜውሮ እምላዕሉ ለደብተራ ። | ፲፪ | ከድንኳኑም በላይ ዓሥራ አንድ መጋረጃዎችን ከፍየል ጠጕር አደረጉ ። |
| ወለለአሐዱ ዓፀድ ኑኁ ሠላሳ በእመት፣ ወርኀቡ ርብዕ በእመት፣ ለለአሐዱ ዓፀድ ከማሁ በአምጣኒሆሙ ። | ፲፫ | ለያንዳንዱም መጋረጃ ርዝመቱ ሠላሳ ክንድ ለያንዳንዱም መጋረጃ ወርዱ እንዲሁ አራት ክንድ ሁኖ መጠናቸው ትክክል ነው ። |
| ወአኀበሩ ኀምስተ አዕፃደ በበይናቲሆሙ፣ ወሰብዕተ አዕፃደ አኀበሩ በበይናቲሆሙ ። | ፲፬ | አምስቱንም መጋረጆች እርስ በርሳቸው ስድስቱንም መጋረጆች እርስ በርሳቸው አንድ አድርገው አጋጠሙዋቸው ። |
| ወገብሩ ኀምስ መማስጠ ላዕለ ክንፈረ አሐዱ ዓፀድ በጽንፉ በዘየኀብሩ ። | ፲፭ | ከተጋጠሙትም መጋረጆች በአንደኛው መጋረጃ ዘርፍ ላይ አምስ ቀለበቶችን አደረጉ ። |
| ወኀምስ መማስጠ ገብሩ ላዕለ ክንፈረ ዓፀድ ካልእ በዘየኀብሩ ። | ፲፮ | ከተጋጠሙትም መጋረጃዎች በሁለተኛው መጋረጃ ዘርፍ ላይ አምስ ቀለበቶችን አደረጉ ። |
| ወገብሩ ኀምስ ሞፃዳተ ዘብርት በዘየኀብሩ ከመ ይኩን አሐደ ። | ፲፯ | ድንኳኑም አንድ እንዲሆን ያጋጥሙት ዘንድ አምስ የናስ መያዣዎችን ሠሩ ። |
| ወገብሩ ዘይከድኖ ሰሠቅ ማእሰ በግዕ ሕሡየ፣ ወከማሁ ገብሩ ለኵሉ ። | ፲፰ | ለድንኳኑም መደረቢያ የለፋ የበግ ቁርበት አደረጉ፤ ከዚያም በላይ ሌላ መደረቢያ ከአስቆጣ ቁርበት አደረጉ ። |
| ወገብሩ አዕማደ ዘደብተራ እምዕፅ ዘኢይነቅዝ ዘዐሥር በእመት ቆሙ ለአሐዱ ዓምድ፣ ወርኅቡ እመት ወመንፈቀ እመት ። | ፲፱ | ለድንኳኑም ከማይነቅዝ ዕንጨት የሚቆሙትን ሳንቆች አደረጉ፤ ለአንዱም ሳንቃ ርዝመቱ አሥር ክንድ፤ ወርዱ አንድ ክንድ ተኩል ነው ። |
| ወመሰምክተ ሥረዊሁ ክልኤቱ ለአሐዱ ዓምድ፣ እንዘ ይሰመክ አሐዱ ምስለ ካልኡ፣ ወከማሁ ገብሩ ለኵሉ አዕማደ ደብተራ ። | ፳ | ለያንዳንዱም ሳንቃ አንዱን ከሌላው ጋር የሚያያይዙ ሁለት ማጋጠሚያዎች ነበሩ፤ ለድንኳኑም ሳንቆች ሁሉ እንዲሁ አደረጉ ። |
| ወገብሩ ዕሥራ አዕማደ እምገጸ አዜብ ። | ፳፩ | በደቡብም ወገን ሃያ ሳንቆችን አደረጉ ። |
| ወገብሩ ሎሙ ለዕሥራ አዕማድ አርብዐ ስከተታተ ዘብሩር፣ ክልኤቱ ስከተቱ ለአሐዱ ዓምድ በክልኤሆሙ ገጸቲሁ ወክልኤቱ ስከተቱ ለአሐዱ ዓምድ በክልኤሆሙ ገጸቲሁ ። | ፳፪ | ለሃያውም ሳንቆች አርባ የብር እግሮችን አደረጉ፤ ለአንድ ሳንቃ በሁለት ወገኑ ሁለት እግሮች በአንድ ወገኑም ሁለት እግሮች ነበሩት፤ ከያንዳንዱም ሳንቃ በታች ሁለት ማጋጠሚያዎች ሁለት እግሮች ነበሩ ። |
| ወእምከልእ ገጸ ደብተራ መንገለ ሰሜን ገብሩ ዕሥራ አዕማደ ። | ፳፫ | ለድንኳኑ በሁለተኛው ወገን በሰሜን በኩል ሃያ ሳንቆችን አደረጉ ። |
| ወስከተቶሙ አርብዓ ዘብሩር ለለአሐዱ ዓምድ፣ ወክልኤቱ ስከተቱ እምክልኤቱ ገጸቲሁ ። | ፳፬ | ለያንዳንዱም ሳንቃ አርባ የብር እግሮች አደረጉ፤ ከእያንዳንዱም ሳንቃ በታች ሁለት እግሮች አደረጉ ። |
| ወእምድኅር እምገጸ ደብተራ መንገለ ባሕር ገብሩ ሰብዓተ አዕማደ ። | ፳፭ | በምዕራብም በኩል በስተኋላ ከድንኳኑ ፊት ለፊት ሰባት ሳንቆችን አደረጉ ። |
| ወክልኤተ አዕማደ ገብሩ ዓዲ ለመዓዝን ተብተራ እምድኅር ። | ፳፮ | ዳግመኛም ለማደሪያው ከሁለት ማዕዝን በስተኋላ ሁለት ሳንቆች አደረጉ ። |
| ወዕሩየ ኮኑ ወኀብሩ እምታሕቱ እስከ ላዕሉ፣ ወከማሁ ገብሩ ለክልኤሆን መዓዝን ። | ፳፯ | ትክክል የሆኑ ከታችም እስከ ላይ እስከ አንደኛው ቀለበት ድረስ አንድ ሳንቃ ድርብ ነበረ፤ ለሁለቱም ማዕዝን እንዲሁ አደረጉ ። |
| ወኮኑ ሰመንቱ አዕማድ ወምዕማዲሆሙ ዓሡሩ ወስሱ ዘብሩር፣ ወለለአሐዱ አሐዱ ዓምድ ክልኤቱ ክልኤቱ ምዕማዱ ። | ፳፰ | ስምንት ሳንቆችና ዓሥራ ስድስቱ የብር እግሮቻቸው ከእያንዳንዱ ሳንቃ በታች ሁለት ሁለት እግሮች ነበሩ ። |
| ወገብሩ መናሥግተ ለአዕማደ ደብተራ እምዕፅ ዘኢይነቅዝ ። | ፳፱ | ለድንኳኑ ሳንቆች ከማይነቅዝ ዕንጨት መወርወሪያዎችን አደረጉ ። |

፴ ኀምስተ መናሥግተ እምአሐዱ ገጽ ወኀምስተ መናሥግተ እምክልኢ ገጽ ፡ ወኀምስተ መናሥግተ ዘመንገለ ባሕር።

በማደሪያውም በአንደኛው ወገን አምስት መወርወሪያዎች በሁለተኛውም ወገን አምስት መወርወሪያዎች በምዕራቡም ወገን አምስት መወርወሪያዎችን አደረጉ ።

፴፩ ወገብሮ ለመንሥግ ዘማእከል ከመ ይዕዱ በማእከለ አዕማድ እምጽንፍ ኀበ ጽንፍ ።

መካከለኛውንም መወርወሪያ በሳንቆቹ መካከል ከዳር እስከ ዳር እንዲያልፍ አደረገው ።

፴፪ ወለአዕማድ ወለመማስጡ ወለመናሥግቲሁ ቀፈል ዎሙ ወርቀ ።

ሳንቆቹንም ቀለበቶቹንም መወርወሪያዎቹንም በወርቅ ለበጡዋቸው ።

፴፫ ወገብሩ መንጦላዕተ ዘያክንት ወኅብረ ክብድ ፡ ወለይ ክዑብ ፡ ወቢሦስ ፍቱል ፡ ወገብሩ በግብረ ምእናም ኪሩቤነ።

መጋረጃውንም ከሰማያዊ ከሐምራዊ ከተፈተለ ቀይ ሐርና ከጥሩ በፍታ በርሱም ላይ በሸማኔነት አሠራር ኪሩቤልን አደረጉበት ።

፴፬ ወገብሩ ላቲ አርባዕተ አዕማደ ዕምዕፅ ዘኢይነቅዝ ፡ ወቀፈልዎሙ ወርቀ ወአርእስቲሆሙኒ ዘወርቅ ።

ከማይነቅዝም ዕንጨት አራት ምሰሶዎችን አደረጉላት በወርቅም ለበጡዋቸው ፡ ኵላቦቻቸውም የወርቅ ነበሩ ።

፴፭ ወገብሩ ሎሙ አርባዕተ ምእማደ ዘብሩር ።

ለነሱም አራት የብር ምዕማዶች (እግሮች) አደረጉ ።

፴፮ ወገብሩ ላቲ መንጦላዕተ ዘይከድኖ ለኆኅተ ደብተራ ፡ እምያክንት ወኅብረ ክብድ ወለይ ክዑብ ፡ ወቢሦስ ፍቱል በብዑድ ግብረት ።

የድንኳኑንም ደጃፍ የሚሸፍን ከሰማያዊና ከሐምራዊ ከቀይ ግምጃና ከተፈተለም ከጥሩ በፍታ በልዩ አሠራር የተሠራ መጋረጃን አደረጉ ።

፴፯ ወገብሩ ላቲ ለመንጦላዕት ኀምስተ አዕማደ እምዕፅ ዘኢይነቅዝ ፡ ወቀፈልዎሙ ወርቀ ፡ ወአርእስቲሆሙኒ ዘወርቅ ፡ ወገብሩ ሎሙ ኀምስተ ምዕማደ ዘብርት ።

ለመጋረጃውም ከማይነቅዝ ዕንጨት አምስት ምሰሶዎች አደረጉላት በወርቅም ለበጡዋቸው ኵላቦቻቸውም የወርቅ ናቸው አምስት የናስ እግሮችንም አደረጉላቸው።

ምዕራፍ ፴፯ ።

፩ ወገብረ ባስልኤል ታቦተ እምዕፅ ዘኢይነቅዝ ዘካዕበ እመት ወመንፈቀ እመት ኑኃ ፡ እመት ወመንፈቀ እመት ራኅብ ፡ እመት ወመንፈቀ እመት ቆሙ ።

ባስልኤል ከማይነቅዝ ዕንጨት (ግራር) ታቦትን ርዝመቱ ሁለት ክንድ ተኩል ፡ ወርዱም አንድ ክንድ ተኩል ቁመቱም አንድ ክንድ ተኩል ሠራ ።

፪ ወቀፈላ ወርቀ ንጹሐ እምውስጣ ወእምአፍአሃ ፡ ወገብረ ላቲ ቀጸላ ወርቅ በዓውዳ ፡ ወገብረ በውስቴታ ማዕበለ ዘወርቅ ዘኖፃዳት እምዓውዳ ።

በውስጥም በአፍአም በጥሩ ወርቅ ለበጣት ፡ በዙርያዋም የወርቅ አክሊል አደረገላት ፡ በዙርያዋ ላሉ ቀለበቶች መቋሚያ ሊሆን ለከንፈርዋ የወርቅ ፈሰስ አወጣላት ።

፫ ወሰበከ ላቲ ዕበነ አርባዕተ ዘወርቅ ወአንበሮን ላዕለ አርባዕቱ ምስማከቲሃ ፡ ዕበነ ክልኤ ውስተ አሐዱ ምስማክ ፡ ወዕበነ ክልኤ ውስተ ዳግም ምስማክ ።

አራት የወርቅ ቀለበቶችንም አደረገላት ፤ ባራት እግሮቿም አኖራቸው ፡ በአንድ ወገን ሁለት ቀለበቶች በሌላውም ወገን ሁለት ቀለበቶች ።

፬ ወገብረ ላቲ መፃውርተ እምዕፅ ዘኢይነቅዝ ወቀፈሎሙ ወርቀ ።

መሎጊያዎቹንም ከማይነቅዝ ዕንጨት ሠርቶ በወርቅ ለበጣቸው ። ዘኍ ፡ ፬ ፯ ።

፭ ወአብአ ድንባዘቲሃ ውስተ እልኩ ዕበን አርባዕ ፡ እለ ውስተ ምስማክ ዘታቦት ፡ መሳክሚሃ ለታቦት በዘይሰክምዋ በሙ ።

ታቦቷንም በነሱ ለመሸከም በታቦቱ አጠገብ ባሉቱ አራት ቀለበቶች መሎጊያዎቹን አገባ ።

፮ ወገብረ ላቲ ተድባበ ዘወርቅ ንጹሕ ፡ ዘካዕበ እመት ወመንፈቀ እመት ኑኁ ፡ እመት ወመንፈቀ እመት ራኅቡ ።

መክደኛውንም ከጽሩ ወርቅ ሠራ ፡ ርዝመቱም ሁለት ክንድ ተኩል ፡ ወርዱም አንድ ክንድ ተኩል ነው ።

፯ ወገብረ ላቲ ክልኤተ ኪሩቤነ ዘወርቅ ፍሑቅ ፡ ወገብሮሙ እምክልኤቱ ምስማከቲሁ ለተድባብ አሐዱ ኪሩብ እምለፌ ፡ ወአሐዱ ኪሩብ እምለፌ እምስማከቲሁ ለተድባብ ።

ሁለቱንም ኪሩቤል ከተመታ ወርቅ ሠራ ፡ በመክደኛውም ላይ በሁለት አደረጋቸው ፡ ከሥርየት መክደኛውም ጋር አንዱን ኪሩብ በአንድ ወገን ሁለተኛውን ኪሩብ በሌላው ወገን አድርጎ በአንድ ላይ ሠራቸው ።

፰ ወከኑ ኪሩቤን ይረብቡ ክነፊሆሙ እመልዕልት እንዘ ይጼልሉ ክነፊሆሙ መልዕልተ ተድባብ ፡ ወገጾሙ ይትናጸር በበይናቲሆሙ በዲበ ተድባብ ።

ኪሩቤልም ክንፎቻቸውን ወደ ላይ ዘርግተው የሥርየት መክደኛውን በክንፎቻቸው ሸፈኑ ፡ እርስ በርሳቸውም በመክደኛው ላይ ፊት ለፊት ይተያያሉ ።

፱ ወገብረ ማእደ እምዕፅ ዘኢይነቅዝ ኑኁ ካዕበ እመት ፡ ወራኅቡ እመት ፡ ወቆሙ እመት ወመንፈቀ እመት ።

ከማይነቅዝም ዕንጨት ርዝመቱ ሁለት ክንድ ወርዱም አንድ ክንድ ፡ ቁመቱም አንድ ክንድ ተኩል የሆነ ገበታን (ማእድን) ሠራ ። ሚል ፡ ፩ ፯ - ፲፪ ።

፲ ወቀፈሎ ወርቀ ንጹሐ ፡ ወገብረ ሎቱ ቀጸላ ዘወርቅ በዓውዱ ።

በጥሩ ወርቅም ለበጠው በዙርያውም የወርቅ አክሊል አደረገለት ።

| | | |
|---|---|---|
| ወገብረ ማዕበለ ዘወርቅ በዓውዱ መጠነ አርባዕቱ አፃባዕ፣ ወገብረ ለቀጸላሁ ዕበነ አርባዕተ፣ ወገብረ ኆፃዳተ ዘማዕበል ለቀጸላሁ ። | ፲፩ | በዙርያውም አንድ ጋት የሚያኽል የወርቅ ፈሰስ አዘረበት በክንፈሩም ዙርያ አራት ቀለበቶችን አደረገለት፣ ለክፈፉም መያዣዎችን ሠራለት ። |
| ወገብረ አርባዕተ አውቃፋተ ዘወርቅ፣ ወአንበሮን ዲበ አዕባን ውስተ አርባዕቱ ፍና፣ ዘአገሪሁ መንገለ ቀጸላሁ ። | ፲፪ | ለአክሊሉም አራት ቀለበት አደረገለት፣ ቀለበቶቹንም አራቱ እግሮቹ ባሉበት በአራቱ ማዕዘኖች አኖራቸው ። |
| ወከኑ አዕባኒሁ አብያተ ለመፃውሪሁ ዘያነሥኡ ማእደ ፤ | ፲፫ | ገበታውንም ለመሸከም መሎጊያዎቹ እንዲሸከሙበቸው ቀለበቶች በክፈፉ አጠገብ ነበሩ ። |
| ወገብረ መፃውርቲሁ እምዕፀ ዘኢይነቅዝ፣ ወቀፈሎሙ ወርቀ ንጹሐ ከመ ያንሥኡ በሙ ማእደ ። | ፲፬ | ገበታውን ይሸከሙበቸው ዘንድ መሎጊያዎቹንም ከማይነቅዝ ዕንጨት ሠርቶ በጥሩ ወርቅ ለበጣቸው ። |
| ወገብረ ንዋያተ ዘማእድ መጽብሐ፣ ወአጽሕልተ፣ ወመዳምሀ፣ ወመዋጽሐ በዘበቱ ያወጽሑ ዘወርቅ ። | ፲፭ | ለማፍሰሻም ይሆኑ ዘንድ በገበታው ላይ የሚኖሩትን ዕቃዎች ወጭቶችን ጭልፋዎችን ጽዋዎችን መቅጃዎችን ከጥሩ ወርቅ ሠራቸው ። |
| ወገብረ መራናተ እምወርቅ ንጹሕ ፍሕቆ፣ ገብረ ለመራናት ዓምዳ ወአብራዒሃ፣ ወመአኅዚሃ፣ ወክበበ ርእሳ፣ ወጽጌያቲሃ እምኔሃ ተገብሩ ። | ፲፮ | መቅረዞችንም ከተመታ ጥሩ ወርቅ አደረጋቸው መቅረዙንም ከእግሩና ከአገዳው ጋር ዕዋዎቹ ጕብጕቦቹና አበቦቹ ከዚያው ተሠሩ ። |
| ሰብዓቱ አብራዕ እለ ይወጽኡ እምገቦሃ ለተቅዋመ ማኅቶት፣ ሠለስቱ አብራዕ እምአሐዱ ፍናሃ፣ ወሠለስቱ አብራዕ እምክልኤ ፍናሃ ። | ፲፯ | ለመብራቱም መቅረዝ በስተጐኑ ሰባት ቅርንጫፎች ወጡለት፣ ሦስቱ ቅርንጫፎች በአንድ ወገን ሦስቱም ቅርንጫፎች በአንድ ወገን ወጡ ። |
| ወሠለስቱ መአኅዚሃ እለ የኃብሩ ምስሌ ለአሐዱ ክበበ ርእስ ጽጉይ፣ ከማሁ ለሰብዓቲሆሙ አብራዕ፣ እለ ይወጽኡ እምተቅዋመ ማኅቶት ። | ፲፰ | በአንደኛው ቅርንጫፍ ጕብጕቡንና አበባውን ሦስትም የለውዝ አበባ የሚመስሉትን ዕዋዎች በሁለተኛው ቅርንጫፍ ጕብጕቡንና አበባውን እንዲሁም ከመቅረዙ ለሚወጡ ለሰባቱ ቅርንጫፎች አደረገ ። |
| ወለተቅዋመ ማኅቶት መአኃዚሃ አርባዕቱ፣ ወጽጌያቲሃ ወክበበ ርእሳ ወክበብ መትሕተ ክልኤቱ ። | ፲፱ | በመቅረዙም ጕብጕቦቹንና አበቦቹን አራትም የለውዝ አበባ የሚመስሉትን ጽዋዎች አደረገ ። |
| ክበበ ርእሳ ወአብራዒሃ እምኔሃ ኮኑ ኵሎሙ ፍሑቀ እምአሐዱ ወርቅ ንጹሕ ። | ፳ | ጕብጕቦችና ቅርንጫፎቹም ከርሱ ጋር አንድ ነበሩ፣ ሁሉም አንድ ሁኖ ከተቀረፀ በጥሩ ወርቅ ተሠርቶ ነበር ። |
| ወገብረ መኃትዊሃ ሰብዓተ፣ ወገብረ ዕዋዓቲሃ ወበዘያሜንይዋ ዘወርቅ ወለኵሉ ንዋያቲሃ መክሊተ ወርቅ ገብራ ። | ፳፩ | ሰባቱንም መብራቶች ዕዋዎችንም መኰስተሪያዎቹንም የኵስታሪ ማድረጊያዎቹንም ከጥሩ ወርቅ ሠራ መቅረዙንም ዕቃውንም ሁሉ ከአንድ መክሊት ጥሩ ወርቅ አደረገ ። |
| ወገብረ ምሥዋዐ ዘዕጣን እምዕፀ ዘኢይነቅዝ ዘእመት ኑኁ፣ ወእመት ራኅቡ፣ ርቡዐ ገብሮ ። | ፳፪ | ከማይነቅዝም ዕንጨት ርዝመቱ አንድ ክንድ ስፋቱ አንድ ክንድ አራት ማዕዘን የሆነ የዕጣን መሠውያን ሠራ ። |
| ወካዕበ እመት ቆሙ፣ ወእምኔሁ ተገብሩ አቅርንቲሁ ። | ፳፫ | ከፍታውም ሁለት ክንድ ነበረ፣ ቀንዶቹም ከሱ ጋር የተሠሩ ነበሩ ። |
| ወቀፈሎ ወርቀ ንጹሐ ምድሮ ወዓውደ አረፍቱ፣ ወአቅርንቲሁ ። | ፳፬ | ላይኛውንና የግድግዳውን ዙርያ ቀንዶቹንም በወርቅ ለበጠው ። |
| ወገብረ ሎቱ ቀጸላ ዘወርቅ በዓውዱ፣ ወክልኤተ አውቃፋተ ወርቅ ገብረ ሎቱ መትሕተ ቀጸላሁ ላዕለ ክልኤቱ ገበዋቲሁ፣ ዘይከውኑ አብያተ ለመፃውሪሁ ከመ ያንሥኡ በሙ ኪያሁ ። | ፳፭ | በዙርያውም የወርቅ ክፈፍ አደረገለት፣ ከክፈፉም በታች ሁለት የወርቅ ቀለበቶች ሠርቶ በሁለት ጐኑ አደረጋቸው፣ እሱን ያነሡበቸው ዘንድ ለመሎጊያዎቹ ስራፍ ነበሩ ። |
| ወገብረ መፃውርቲሁ እምዕፀ ዘኢይነቅዝ፣ ወቀፈሎሙ ወርቀ ። | ፳፮ | መሎጊያዎቹንም ከማይነቅዝ ዕንጨት ሠርቶ በወርቅ ለበጣቸው ። |
| ወገብረ ቅብዐ ዘይትቀብዑ እምዘይት፣ ወአፈዋተ ቅድወ፣ ጽሑጠ ዘጸዐጢ ። | ፳፯ | የሚቀቡትንም ቅባት ከዘይት አደረገ፣ ጥሩውንም የጣፋጭ ሽቱ ዕጣን በቀማሚ ብልሃት የተቀመመ አደረገ። |
| ምዕራፍ ፴፰ ። | | ምዕራፍ ፴፰ ። |
| ወገብረ ምሥዋዐ ለመሥዋዕት እምዕፀ ዘኢይነቅዝ ዘኀምስቱ በእመት ኑኁ፣ ወኀምስቱ በእመት ራኅቡ፣ ርቡዐ ኮነ፣ ወሠልስ በእመት ቆሙ ። | ፩ | ርዝመቱ አምስት ክንድ፣ ወርዱም አምስት ክንድ ለሚቃጠል መሥዋዕት የሚሆን ከማይነቅዝ ዕንጨት ሠራ ከፍታውም ሦስት ክንድ ሆኖ አራት ማዕዘን ነበር ። |

፪ ወገብረ አእጋሪሁ ውስተ አርባዕቱ መዓዝኒሁ ወእምኔሁ ይእቲ ምቅዋማቲሁ ።

፫ ወገብረ ሎቱ አቅርንተ ዲበ አርባዕቱ መዓዝኒሁ፤ ወእምኔሁ ወጽአ አቅርንቲሁ ወቀፈሎ ብርተ ።

፬ ወገብረ ኵሎ ንዋያተ ምሥዋዕ ምግኅሣተ፤ ወጸኅራተ ወፍያላተ ወመኅፈስተ ወመሰውደ እሳት ኵሎ ገብረ እምብርት ።

፭ ወገብረ መጥበስተ ለመሥዋዕት ስቅሉቀ፤ ከመ መሥገርተ ዓሣ ዘብርት ።

፮ ወገብረ ሎቱ ለመጥበስት አርባዕተ ኅልቀታተ ዘብርት ውስተ አርባዕቱ መዓዝኒሁ ።

፯ ወአንበሮ ለመጥበስት በቤተ መሥዋዕት ታሕተ ወከነ በመንፈቀ ቤተ መሥዋዕት ።

፰ ወሰበከ አርባዕተ አውቃፋተ ዘብርት ለአርባዕቱ መዓዝኒሁ ከመ ይኩኑ አብያተ ለመፃውርቲሁ ።

፱ ወገብረ መፃውርተ እምዕፅ ዘኢይነቅዝ፤ ወቀፈሎሙ ብርተ ወአብአ መፃውርቲሁ ውስተ አውቃፋት ዘላዕለ ገበዋቲ ምሥዋዕ ከመ ያንሥኡ በሙ ኪያሁ ፍሉግ ሰሌዳ ገብሮ ።

፲ ወገብረ ማእከከ ዘብርት ወመንበሩሂ ዘብርት፤ ወአንበሮ በአንጻረ አንስት እለ ይመጽኣ ከመ ይጸልያ ኀበ አንቀጸ ደብተራ ዘመርጡል በዘይትሐፀቡ ቦቱ ።

፲፩ ወገብረ ላቲ ዐፀደ ለደብተራ መንገለ አዜብ እንተ የማን ወመንጦላዕተ ዓፀድ እምቢሶስ ክሩብ ወኑኁ ምእት በእመት ።

፲፪ ወአዕማዲሁ ዕሥራ ዘብሩር ወምዕማዲሆሙ ዕሥራ ዘብርት ።
ውኖፃዲቲሆሙ ወጥነፊሆሙ ለአዕማድ ዘብሩር ።

፲፫ ወለመንገለ ሰሜን መንጦላዕቱ ምእት በእመት ኑኁ ።

፲፬ ወአዕማዲሁ ዕሥራ ዘብሩር ወምዕማዲሆሙ ዕሥራ ዘብርት ውኖፃዲቲሆሙ ወጥነፊሆሙ ለአዕማድ ዘብሩር ።

፲፭ ወዘመንገለ ባሕር መንጦላዕቱ ኃምሳ በእመት ኑኁ፤ አዕማዲሆሙ ዐሠርቱ ዘብሩር ወምዕማዲሆሙ ዐሠርቱ ዘብርት ።

፲፮ ውኖፃዲቲሆሙ ወጥነፊሆሙ ለአዕማድ ዘብሩር ።

፲፯ ወዘመንገለ ጽባሕ መንጦላዕቱ ኃምሳ በእመት ኑኁ፤ ወአዕማዲሁ ዐሠርቱ ዘብሩር፤ ወምዕማዲሆሙ ዐሠርቱ ዘብርት ።

፲፰ ዐሠርቱ ወኀምስቱ በእመት ኑኁ ለመንጦላዕት እምገጸ አሐዱ ምስማክ፤ አዕማዲሁ ሠለስቱ፤ ወምዕማዲሆሙ ሠለስቱ ።

፲፱ ወእምካልእ ምስማክ፤ ዐሠርቱ ወኀምስቱ በእመት ኑኁ ለመንጦላዕት፤ አዕማዲሁ ሠለስቱ ወምዕማዲሆሙ ሠለስቱ፤ ወኵሉ መንጦላዕተ ዓፀድ ዘዓውድ እምቢሶስ ።

፳ ወኵሉ አዕማድ ዘዐፀድ ወአርእስቲሆሙ ቅሩላን በብሩር፤ ወምዕማዲሆሙ ዘብርት ።

እግሮቹንም በአራት ማዕዘኑ አደረገ፤ ማቆሚያዎቹም ከርሱ ጋር አብረው የተሠሩ ነበሩ ።

ቀንዶችንም በአራት ማዕዘኑ አደረገለት፤ ቀንዶቹም ከርሱ ጋር በአንድነት የተሠሩ ናቸው፤ በናስም ለበጠው ።

የመሠውያዎቹንም ዕቃዎች ሁሉ፤ ምንቸቶቹን መጫረፊያዎቹን፤ ድስቶቹን፤ ሜንጦቹንና የእሳት ማንደጃዎቹን ሁሉ ከናስ አደረገ ።

እንደ ዓሣ መረብ ሁኖ የተሠራም ለመሠውያው መጥበሻ የናስ መከታ አደረገ ።

ለመጥበሻውም አራት የናስ ቀለበቶችን በአራት ማዕዘኑ አደረገለት ።

መከታውንም እስከ መሠውያው እኩሌታ ይደርስ ዘንድ ከመሠውያው ቤት በታች አኖረው ።

ለመሎጊያዎቹም ሥፍራ ይሆኑ ዘንድ ለአራቱ ማዕዘኖች አራት የናስ ቀለበቶችን ሠራ ።

መሎጊያዎቹን ከማይነቅዝ ዕንጨት ሠርቶ በናስ ለበጣቸው፤ መሎጊያዎቹንም እሱን ይሸከሙበቸው ዘንድ በመሠውያው ጐን ላይ ባሉት ቀለበቶች ውስጥ አገባ፤ ከሳንቆቹም ሠርቶ ክፍት አደረገው ።

መቀለዱንና እግር ዘቀኑነውን ከናስ ሠርቶ (ሴዋውያን) በሚታጠቡበት በደብተራ ኦሪት ደጃፍ ሊጸልዩ በሚመጡ ሴቶች አንጻር አኖረው ።

ለደብተራ ኦሪት በስተደቡብ በቀኝ በኩል አደባባይ ሠራ፤ የአደባባዩም መጋረጃ ርዝመቱ መቶ ክንድ የሆነ፤ ዕፅፍ ሁኖ ከተፈተለ ብጫ ሐር የተሠራ ነው ።

ሃያ የብር ምሰሶዎችንና ሃያ የብርት ምዕማዶችን ሠራ ።

ለምሰሶዎቹም ኩላቦቻቸውንና ዘንጎቻቸውን ከብር አደረገ ።

በስተ ሰሜንም መቶ ክንድ ርዝመት ያለው መጋረጃ አደረገ ።

ሃያ የብር ምሰሶዎችንና የናስ እግሮችንም ሠራ፤ ለምሰሶዎቹም የብር ኩላቦችንና ዘንጎችን አደረገ ።

በስተ ምዕራብም ርዝመቱ አምሳ ክንድ ያለውን መጋረጃ ሠራ፤ ዓሥር ምሰሶዎቹ ከብር፤ ዓሥር እግሮቹ ከናስ የተሠሩ ነበሩ ።

የምሰሶዎቹም ኩላቦችና ዘንጎች የብር ነበሩ ።

በስተ ምሥራቅም ርዝመቱ አምሳ ክንድ ያለውን መጋረጃ ሠራ፤ ከብር የተሠሩ ምሰሶዎቹ ዓሥር ከናስ የተሠሩ እግሮቹም ዓሥር ነበሩ ።

በአንዱም ወገን ርዝመቱ ዓሥራ አምስት ክንድ ምሰሶዎቹም ሦስት ምዕማዶቹም ሦስት ነበሩ ። ፪ ዜና፡ ፫ ፲፬ ።

በሁለተኛውም ወገን ርዝመቱ ዓሥራ አምስት ክንድ ያለውን መጋረጃ አደረገ፤ ምሰሶዎቹም ሦስት የምሰሶዎቹ ምዕማድም ሦስት ነበሩ፤ በአደባባዩ ዙርያ ያለው መጋረጃ ሁሉ ከጥሩ በፍታ የተሠራ ነው ።

የአደባባዩም ምሰሶች ሁሉና ክበሰቻቸው በብር የተለበጡ ነበሩ፤ ምዕማዶቻቸውም ከናስ የተሠሩ ናቸው ።

| | | |
|---|---|---|
| ወአእንቃጸ ዓፀድ መንጦላዕቱ ዕሥራ በእመት ኑኁ፤ በያክንት ወኅብረ ክብድ ወለይ ክዑብ ወቢሦስ ክዑብ ወብ ዑደ ከነ በግብረ መርፍእ ። | ፳፪ | ሃያ ክንድ የሆነ የአደባባዩም ደጅ መጋረጃ ከሰማያ ዊና ከሐምራዊ ሐር፥ ከቀይ ግምጃ ከጥሩ በፍታም በልዩ ጥልፍ አሠራር የተሠራ ነበር ። |
| ወቆሙ ኃምስቱ በእመት እመንገለ ራኀቡ ከመ መን ጦላዕተ ዐፀድ ። | ፳፫ | ርዝመቱ አምስት ክንድ፥ ቁመቱም እንደ አደባባዩ መጋረጃ አምስት ክንድ ነበር ። ዘፀ፡ ፳፯ ፱-፲ ። |
| ወአዕማዲሁ አርባዕቱ ዘብሩር ወምዕማዲሆሙ አርባ ዕቱ ዘብርት፤ ወኵሉ መታክለ ደብተራ ዘዐውደ ዓፀድ ዘብርት ። | ፳፬ | አራት ምሰሶዎቹ ከብር አራት ምዕማዶቹም ከናስ የተ ሠሩ ነበሩ፤ በደብተራ አሪት ዙርያ ያሉ ካስማዎች ሁሉ የናስ ነበሩ ። |
| ወኪመዝ ሥርዓታ ለደብተራ መርጡል ዘከመ ተአዘዘ ሙሴ እምእግዚአብሔር ከመ ይኩኖሙ ግብሮሙ ለሌዋ ውያን በእደ ይታምር ወልደ አሮን ክህን ። | ፳፭ | ሙሴ ከእግዚአብሔር እንደ ታዘዘው ለሌዋውያን ማገ ልገያ እንዲሆናቸው በካህኑ በአሮን ልጅ በይታምር የተ ቈጠረው የደብተራ አሪት ዕቃ ድምር ይህ ነው ። ዘሌ ፰ ፲፰፣ |
| ወባስልኤል ወልደ ኡሪ ወልደ ሖር ዘእምነገደ ይሁዳ ገብረ ኵሎ በከመ አዘዞ እግዚአብሔር ለሙሴ ። | ፳፮ | ከነገደ ይሁዳ ወገን የሆነ የሖር የልጅ ልጅ የኡሪ ልጅ ባስልኤል እግዚአብሔር ለሙሴ እንዳዘዘው ሁሉን ሠራ ። |
| ወምስሌሁ ኤልያብ ወልደ አክሴምክ ዘእምነገደ ዳን ዘከነ ሊቀ ኪነት ዘበምእናም ወዘበመርፍእ ወበዘአሥቅ፤ ከመ ይእንም በያክንት ወበኅብረ ክብድ ወበለይ ክዑብ ወቢሦስ ክዑብ ። | ፳፯ | በሽማኔነት በግብረ መርፌና በጥልፍ ሥራ የጥበብ አ ለቃ የሆነ የዳን ነገድ ወገን የአክሴምክ ልጅ ኤልያብም በሰማያዊ በሐምራዊ ዕፅፍ ሁኖ በተፈተለ ቀይ ግምጃና በብጫ ሐር ይሠራ ዘንድ ከርሱ ጋር ነበር ። |
| ወኵሉ ወርቅ ዘመበእ ዘተገብረ ለምግባረ ደብተራ፤ ከነ ዕሥራ ወተስዓቱ መክሊይ ወሰብዑቱ ምእት ወሠ ላሳ ሰቅል በሰቅል ቅዱስ ። | ፳፰ | የደብተራ አሪት ሥራ የተሠራበት የመባው ወርቅ ሁሉ በቤተ እግዚአብሔር አዋቂ ሚዛን ሃያ ዘጠኝ መክ ሊት ሰባት መቶ ሠላሳ ወቄት ሆነ ። ዘፀ፡ ፳፯ ፲፱-፳፩ ። |
| ወብሩርኒ ዘመበእ ዘአስተፋቀዱ እምትዕይንት፤ ምእ ት መክሊይ፡ ወዓሠርቱ ምእት ወሰብዓቱ ምእት ሰብዓ ወኃምስቱ ሰቅል በሰቅል ቅዱስ ። | ፳፱ | ከከተማው አቆጣጥረው ያመጡት እስራኤል መባ አድ ርገው ያቀረቡት ብርም በመቅደሱ ሰቅል ሚዛን መቶ መክ ሊት፤ ሺሕ ሰባት መቶ አምስት ወቄት ሆነ ። |
| ዘአስተዋድኡ በበርእሶሙ አሐተ አሐተ ዲድርክመ፤ ወአሐቲ ዲድርክም መንፈቀ ሰሰቅል ። | ፴ | በየራሳቸው ያዋጡትም ገንዘብ አንድ አንድ ወቄት ነው ይኸውም አንድ ድሪም አቀመት የሰቅል ግማሽ ነው ። |
| ወኵሉ ፡ሐረ ውስተ ፍቅድ ዘእምዕሥራ ዓም ወላ ዕሉ ስሳ እልፍ ወሠላሳ ምእት ወኃምስቱ ምእት ወኃምሳ ። | ፴፩ | ይህንም ገንዘብ ለመስጠት ሊቈጠር የሄደው ሰው ከ ሃያ ዓመት ጀምሮ ከዚያም በላይ የሆነው ስሳ እልፍ ከሦ ስት ሺሕ አምስት መቶ አምሳ ነበር ። |
| ወተገብረ ዝክቱ ምእት መክልይ ዘብሩር ለምዕማደ አዕማድ ዘደብተራ፤ ወለምዕማደ አዕማድ ዘመንጦላዕት ። | ፴፪ | ይኸውም መቶው የብር መክሊት ለደብተራ አሪት ምሰሶዎች ክባስ ለመጋረጃው ምሰሶዎችም እግር ተሠ ሩላቸው ። ዕዝ፡ ፱ ፷፤ ኢሳ፡ ፳፪ ፳፬ ። |
| ምእት መክልይ ለምእት ምዕማድ፤ በበሐቲ መክሊት ለሰሐቲ ርእስ ። | ፴፫ | ይህም መቶው መክሊት ለመቶው ክባሶች ለያንዳን ዲቱ መክሊት በያንዳንዲቱ ራስ ላይ ነው ። |
| ወሰዝክቱ ዐሠርቱ ምእት ወሰብዐቱ ምእት ወሰብዓ ወኃምስቱ ሰቅል ገብርዎ ለአዕማደ ዓፀድ ። | ፴፬ | ይህንም ሺሕ ከሰባት መቶ ሰባ አምስቱን ወቄት ለዙ ርያ ቅጥሩ አዕማድ ክባስ አድርገው ሠሩት ። |
| ወከነ ብርት ዘመበእ አርባዕቱ ምእት ወሰብዓ መክልይ ወዕሥራ ምእት ወአርባዕቱ ምእት ሰቅል ። | ፴፭ | ለእግዚአብሔር መባ ሆኖ የገባው ብርቱም አራት መቶ ወቄት ሁለት ሺሕ አራት መቶ ሰቅል ነው ። |
| ወገብረ እምኔሁ መንበረ ኆኅተ ደብተራ ዘመርጡል ወምሥዋዐ ዘመሥዋዕት ። | ፴፮ | ሙሴም ከዚህ ብረት ለደብተራ አሪት ደጃፍ መድረክ መሥዋዕት የሚሠዋበትን መሠውያንን አደረገ ። |
| ወመጥበስተ ወኵሎ ንዋየ ምሥዋዕ ወመንበረ ዓፀድ ዘዓውድ ። | ፴፯ | መሥዋዕቱ የሚጠበስበት መጥበስትን፤ የምሥዋዑን ሥራ ሁሉ ሠራበት ። |
| ወመንበረ አንቀጸ ዓፀድ ወኵሎ መታክለ ደብተራ ወመታክለ ዓፀድ ዘዓውድ ። | ፴፰ | በዙርያው ላለውም ቅጥር አዕማድ፤ ለዙርያ ቅጥሩም በር መድረክ፤ ለደብተራ አሪትም ካስማ በዙርያ ላለው ሽማ ቅጥርም ካስማ ሠራለት ። |

ምዕራፍ ፴፱ ።

ምዕራፍ ፴፱ ።

| | | |
|---|---|---|
| ወዘተርፈ ወርቅ ዘመበእ ተገብረ ንዋየ በዘይገብሩ ቅድመ እግዚአብሔር ። | ፩ | ለመባ ከገባው ወርቅ የተረፈው ወርቅ ግን በእግዚአ ብሔር ፊት በሚሠሩበት ገንዘብ ሌላ ዕቃ ተሠራበት ። |

፪ ወእምነ ያክንት ወኅብረ ክብድ ወለይ ወቢሦስ ተገብረ አልባስ ለመልእክተ መቅደስ ።

፫ ወገብሩ አልባሰ ቅዱሰ ለአሮን በከመ አዘዞ እግዚአብሔር ለሙሴ ።

፬ ወገብሩ ኤፉደ በወርቅ ወበያክንት ወበኅብረ ክብድ ወበለይ ክዑብ፣ ወቢሦስ ክዑብ ።

፭ ወገብሩ ቈጽለ ዘወርቅ ወሰጠቅዎ ወገብርዎ ከመ ይትፈተል ምስለ ያክንት ወምስለ ኅብረ ክብድ ወምስለ ለይ ክዑብ ወምስለ ቢሦስ ክዑብ ።

፮ ወገብርዎ ልብሰ መትከፍት ዘይወርድ ውስተ ክልኤሆን መታክፊሁ ወአነሙ ክልኤተ ኢጲሞሰተ እምኔሆሙ እለ ይትላጸቁ በክልኤቱ ገበዋቲሁ ።

፯ ወለትብልያሰ ዘልብሰ መትከፍት አነምዎ እምኔሆሙ በከመ አነሙ ኪያሃ በወርቅ ወበያክንት ወበኅረ ክብድ ወበለይ ክዑብ ወቢሦስ ክዑብ በከመ አዘዞ እግዚአብሔር ለሙሴ ።

፰ ወገብሩ እእባነ መረግድ ወአውደድምሙ ምስለ ወርቅ ወገለፍዎሙ ከመ ግልፈተ ማኅተም በበአስማቲሆሙ ለደቂቀ እስራኤል ።

፱ ወአንበርዎሙ ዲበ ኤጲሞስቲሃ ለልብሰ መትከፍት ለአዕናቍ ዘተዝካሮሙ ለደቂቀ እስራኤል ዘከመ አዘዞ እግዚአብሔር ለሙሴ ።

፲ ወገብሩ ልብሰ ሎግዮ ግብረ ምእናም እሡቅ ከመ ግብረተ ልብሰ መትከፍት በወርቅ ወበያክንት ወበኅብረ ክብድ ወበለይ ክዑብ ወቢሦስ ክዑብ ርቡዕ ወውጡሕ ውእቱ ።

፲፩ ወልብሰ ሎግዮ እመት ኑኑ ወእመት ራኅቡ፣ እንዘ ውጡሕ ውእቱ ወተአንመ ውስቴቱ አርበዕቱ ፆታ እንመት ዘአዕናቍ ።

፲፪ አሐዱ ፆታ በሰርድዮን ወበጳዝዮን ወበመረግድ ።

፲፫ ወካልእ ፆታ ዘኅብሩ ከመ ፍሕም ወሰንፔር ወኢያሰጲድ ።

፲፬ ወሣልስ ፆታ በለግርዮን ወበአካጥስ ወበአሜቴስጢኖስ።

፲፭ ወራብዕ ፆታ በዕንቍ ዘኅብረ ወርቅ ወቢረሌ ወበሦም፣ ወዓውዶሙ በወርቅ እሱር ።

፲፮ ወውእቶሙ አዕናቍ በበአስማቲሆሙ ለዐሠርቱ ወክልኤቱ ደቂቀ እስራኤል ወግሉፋን ከመ ግልፈተ ማኅተም ለለአሐዱ በበስሞሙ ።

፲፯ ወገብሩ ሎቱ ለልብሰ ሎግዮ ሰናስለ ጽፉረ በግብረት ፍቱል ወበወርቅ ንጹሕ ።

፲፰ ወገብሩ ክልኤተ ክበበ ጥውዮ ዘወርቅ፣ ወክልኤተ ኅልቀታተ ወርቅ ወወደይዎን ለውእቶን ኅልቀታት ውስተ ክልኤሆን ጽንፈሁ ለልብሰ ሎግዮ ።

፲፱ ወወደይዎ ለዝክቱ ጽፍሮ ወርቅ ላዕለ እልክቱ ኅልቀታት እልክቱ ኅልቀታት እምክልኤሆሙ ገበዋቲሁ ለልብሰ ሎግዮ ወውስተ ክልኤሆሙ ማኅበርቱ ወክልኤቱ ጽፍር ።

፳ ወአንበርዎን ላዕለ እልክቱ ክልኤ ክበበ ጥውዮ ወወደይዎን ማእከለ መታክፍቲሁ ለልብሰ መትከፍት አንጻረ ገጹ፤

፳፩ ወገብሩ ኅልቀታተ ወርቅ ወአንበርዎሙ ላዕለ ክልኤቱ

ከሰማያዊ ከሐምራዊና ከቀይ ሐር ከብጫ ሐርም በመቅደስ ለማገልገል ልብስ ተሠራ ።

እግዚአብሐር ሙሴን እንዳዘዘውም የተቀደሰውን ልብስ ለአሮን ሠሩለት ።

ኤፉድንም በወርቅ በሰማያዊ ሐር፣ በሐምራዊ ሐር ዕፅፍ ሁና ከተፈተለ ከብጫ ሐርና ከቀይ ግምጃ አደረጉ።

ወርቁንም እንደ ቅጠል አሳስተው እየሰነጠቁ ከሰማያዊ ከሐምራዊ ከቀይና ከብጫ ሐር ጋር እየተሸረበ እንዲፈተል አደረጉት ።

በሁለቱ ጫንቃዎቹ የሚወርድ ልብሰ መትከፍትን ሠሩ፣ ከአራቱ ኅብርም በሁለት ወገኖቹ የሚገናኙ ሁለት ቀሚሶችን ሠሩ ። ኢሳ፣ ፲፩ ፭፣ ራዕ፣ ዮሐ፣ ፩ ፲፫ ።

እግዚአብሔር ሙሴን እንዳዘዘው እጀን በወርቅ በሐምራዊ በሰማያዊ በብጫና በቀይ ግምጃ እንደሠሩ የልብሰ መትከፉን መታጠቂያ አድርገው ሠሩት ።

የመረግድ (ዕንቍ) ደንጊያዎችንም ሠርተው ከወርቅ ጋር አስማምተው እንደ ማኅተም ቅርጽ አድርገው የእስራኤል ልጆች ስም ቀረፁባቸው ። ኢያ፣ ፬ ፯፣ ነሀ፣ ፪ ፳።

ለእስራኤል ልጆች የመታሰቢያ ድንጋዮች ይሆኑ ዘንድ እግዚአብሔር ሙሴን እንዳዘዘው አድርገው ዕንቆቹን በኤፉዱ ጫንቃ ቀሚሶች ላይ አኖሩዋቸው ።

የደረቱን ኪስ እንደ ኤፉድ አሠራር ብልሃት ሥራ በወርቅ በሰማያዊ በሐምራዊ በቀይና በብጫ ሐር ሠሩት፣ ምዕዙንና ድርብም አደረጉት ። ሕዝ፣ ፳፰ ፲፫ ።

የደረቱን ኪስ (ልብሰ ሎግዮ) ድርብ ሁኖ ርዝመቱ ክንድ ወርዱም ክንድ ነበረ፣ በርሱም አራት ተራ የአዕናቍ ፈርጥ አደረጉበት ።

አንደኛው ተራ ሰርድዮን፣ ጳዝዮን መረግድ ።

ሁለተኛው ተራ እንደ ፍም መልክ ያለ ዕንቍ ሰንፔር ኢያሰጲድ ።

ሦስተኛው ተራ በለግርዮን (ያክንት) ኬልቄዶን አሜቴስጢኖስ ።

አራተኛው ተራ ወርቅማ ዕንቍ ቢረሌ ሦም ሲሆኑ እሊህ ሁሉ በወርቅ ፈርጥ የተያዙ ናቸው ።

እነዚህም ዕንቆች በዓሥራ ሁለቱ የእስራኤል ልጆች ስም ለያንዳንዱም በየስማቸው እንደ ማኅተም አቀራረፅ የተቀረፁ ናቸው ።

ለደረቱም ኪስ የተጐነጐኑትን ድሪዎች እንደ ገመድ አድርገው ከጥሩ ወርቅ ሠሩለት ።

ሁለት የወርቅ ፈርጦችን ሁለት የወርቅ ቀለበቶችንም ሠርተው እሊያን ሁለት ቀለበቶች በሁለት የደረት ኪስ ጫፎች አደረጉዋቸው ።

ሁለቱንም የተጐነጐኑትን የወርቅ ድሪዎች በደረቱ ኪስ ወገኖች ወዳሉት ወደ ሁለቱ ቀለበቶች አደረጉ (አገቡ) ።

ሁለቱንም የድሪ ጫፎች በሁለቱ ፈርጦች ውስጥ አግብተው በኤፉድ ጫንቃዎች ላይ ፊት ለፊት አደረጉዋቸው ።

ሁለቱንም የወርቅ ቀለበቶች ሠርተው በኤፉዱ ፊት

| | | |
|---|---|---|
| ዘነፊሁ ለኤፉድ እምታሕቱ መንገለ ገጹ ኀበ ማኅበርቱ መልዕልተ እንመቱ ለልብሰ መትከፍት ። | | ሐፊት ባለው በደረቱ ኪስ በሁለቱ ጫፎቹ ላይ አደረጉዋቸው ። |
| ወአስተአኀዝዎ ለልብሰ ሎግዮ እምኅልቀታቲሁ ኀበ ኅልቀታተ ኤፉድ በፈትለ ያክንት ከመ ይኩን ሳዕለ እንመተ ኤፉድ ፥ ከመ ኢያንጠልል ልብሰ ሎግዮ እምልብሰ መትከፍት ዘከመ አዘዞ እግዚአብሔር ለሙሴ ። | ፳፪ | የደረቱን ኪስ በብልሃት ከተጠለፈው ከኤፉድ ቋድ በላይ እንዲሆን ፥ ከኤፉዱም እንዳይለይ የደረቱን ኪስ ከቀለበቶቹ ጋር ወደ ኤፉዱ ቀለበቶች በሰማያዊ ፈትል አያያዙት እግዚአብሔር ሙሴን እንዳዘዘው ። |
| ወገብሩ ጳዴሬ በግብረ ምእናም ዘኵለንታሁ በያክንት ክዑብ ፥ ወአፈ መልበስቱ እምኔሁ በዓውዱ ወድማሬሁ እንዋ ከመ ኢይትበተክ ። | ፳፫ | ኤፉዱን ቀሚስ ሁለንትናው በሸማኔ ሥራ አሠራር በሰማያዊ ሐር ሠሩት ፥ እንዳይቀደድም እንደ ጥሩር የተሠራ ጥልፍ በአንገትጌው ዙርያ ነበር ። |
| ወገብሩ መልዕልተ ዓውዱ በልብሰ ጳዴሬ መትሕቲሁ ከመ ፍሬያተ ሮማን ሰበ ይጸጊ እምያክንት ወኅብረ ከብድ ወለይ ክዑብ ወቢሶስ ክዑብ ። | ፳፬ | በቀሚሱም ታችኛው ዘርፍ ከሰማያዊ ከሐምራዊ ከቀይ ግምጃና ከጥሩ ሐር እንደ ሮማን ፍሬዎች በዙርያው ላይ አደረጉ ። |
| ወገብሩ ጸናጽላተ እምወርቅ ንጹሕ ወአንበርዎን ለጸናጽላት ማእከለ ሮማናት ዲበ ጽንፉ ለጳዴሬ እንተ ዓውዱ ። | ፳፭ | ከጥሩ ወርቅም ጸናጽሎችን (ቃጭሎችን) ሠርተው ቃጭሎቹን በቀሚሱ ዙርያ ዘርፍ ላይ በሮማኖቹ መካከል አደረጉዋቸው ። |
| ወበውስተ ሮማናት ጸናጽል አሐዱ ወሮማን አሐዱ ጸናጽል አሐዱ ወሮማን አሐዱ ፥ ጸናጽል አሐዱ ወሮማን አሐዱ በዘበቱ ይገብሩ ዘከመ አዘዞ እግዚአብሔር ለሙሴ ። | ፳፮ | እግዚአብሔር ሙሴን እንዳዘዘው የሚያገለግሉበትን አንድ ጸናጽል አንድ ሮማን ፥ አንድ ሮማን አንድ ጸናጽል አከታትለው በሮማኖቹ ውስጥ አደረጉ ። |
| ወገብሩ አልባሰ ዘቢሶስ ግብረ ምእናም ለአሮን ወለደቂቁ ወአክሊለ ዘቢሶስ ፥ ወቆብዐ ዘቢሶስ ፥ ወድርማንቀ ዘቢሶስ ። | ፳፯ | ለአሮንና ለልጆቹ እንደ ሸማኔ አሠራር ከነጭ ሐር መጠምጠሚያን ከነጭ ሐርም ቆብን ከነጭ የተልባ እግር ሰናፊልን ሠሩላቸው ። ኢሳ፥ ፷፩ ፲፥ ሮሜ ፫ ፳፪ ። |
| ወቅናታተ ዘቢሶስ ፥ ወዘያክንት ወዘኅብረ ከብድ ወዘለይ ክዑብ ወእሡቅ ግብሩ ዘከመ አዘዞ እግዚአብሔር ለሙሴ ። | ፳፰ | እግዚአብሔር ሙሴን እንዳዘዘው ከነጭ ሐር ፥ ከሰማያዊ ከሐምራዊ ከቀይ ግምጃ በጥሩ አሠራር የተሠሩ መታጠቂያዎችን ሠሩ ። ዘፀ፥ ፳፰ ፬ ፴፱፥ ሕዝ፥ ፵፬ ፲፰ ። |
| ወገብሩ ቈጽለ ወርቅ ፍሉጠ እምወርቅ ንጹሕ ወጸሐፉ ላዕሌሁ መጽሐፈ በቅርፀተ ማኅተም ቅዱስ ለእግዚአብሔር ። | ፳፱ | ከጥሩ ወርቅ የተለየ (የተቀደሰ) አሳስተው ሠርተው በላዩ ላይ እንደ ማኅተም ቅርፅ ለእግዚአብሔር ቅዱስ መባል ይገባል የሚል ጻፉበት ። ዘፀ፥ ፳፰ ፴፮ ። |
| ወወደዩ ሎቱ ነጽፈ ዘያክንት ከመ ይንበር መልዕልተ አክሊል ዘከመ አዘዞ እግዚአብሔር ለሙሴ ። | ፴ | እግዚአብሔር ሙሴን እንዳዘዘው በመጠምጠሚያው ላይ ያንጠለጥሉት ዘንድ ሰማያዊ ሐር አሠሩበት ። |
| ወተፈጸመ ኵሉ ምግባረ ደብተራ ወገብሩ ደቂቀ እስራኤል ኵሎ ዘከመ አዘዞ እግዚአብሔር ለሙሴ ። | ፴፩ | የደብተራ ኦሪት ሥራ ሁሉ ተፈጸመ ፥ የእስራኤል ልጆችም እግዚአብሔር ለሙሴ ያዘዘውን ሁሉ ሠርተው ፈጸሙ ። |
| ወአምጽእዋ ለደብተራ ኀበ ሙሴ ወለሠቃቲሃ ወለኵሉ ንዋያቲሃ ወለአዕማዲሃ ወለኖኀዳቲሃ ወለመናሥግቲሆን ወለመከየዲሆን ። | ፴፪ | ድንኳኒቱንም ዕቃዎቿን ሁሉ መደረቢያዎቿን ምሰሶዎቿን መያዣዎቿን መወርወሪያዎቿን የምሰሶዎቿን እግሮች ሁሉ ወደ ሙሴ አመጡ ። ዘፀ፥ ፳፭ ፵ ። |
| ወመክደንታቲሃ ዘአምእስተ በግዕ ወአምእስተ መጸጺት ወመንጦላዕተ ምክዳን ወታቦተ ስምዕ ። | ፴፫ | ከአውራ በግ ቁርበት የተሠሩ መደረቢያዎች ከአስቆጣ ቁርበት የተሠሩ ማእሰ መጸጺቶች የሚሸፍነውንም መጋረጃ የምስክሩንም ታቦት ። ዕብ፥ ፱ ። |
| ወመፃውርቲሃ ወምስሐለ ወማእደ ምስለ ኵሉ ንዋያቲሁ ወኅብስተኒ ዘይሠርዑ ። | ፴፬ | መሎጊያዎቿን የሥርየት መክደኛውን ገበታውን ከነ ዕቃዎቹ ሁሉ የሚያቀርቡትንም ኅብስት ። |
| ወተቅዋመ ማኅቶት ንጽሕተ ወመኃትዊሃ ዘየኃትዉ በሙ ወኵሎ ንዋያቲሃ ። | ፴፭ | የጸራውን መቅረዝ የሚያበሩባቸው ቀንዲሎቿን ዕቃዎቿን ሁሉ ። |
| ወቅብዐ ማኅቶት ወምሥዋዐ ዘወርቅ ወቅብዐ በዘይት ቅብዑ ወዕጣነ ዘየዓጥኑ ። | ፴፮ | የመብራቱን ዘይት የወርቅ መሠውያን የሚቀቡትንም ቅብዓ ቅዱስ የሚያጥኑትን ጥሩ ዕጣን ። |
| ወመክደኒ ኆኅተ ደብተራ ወምሥዋዐ ዘብርት ወመጥበሰ ዘብርት ዘሎቱ ወለመፃውርቲሁ ወኵሎ ንዋያቲሁ ። | ፴፯ | የደብተራ ኦሪትን ደጃፍ መጋረጃ የናሱን መሠውያ የናሱን መከታ (መጥበሻ) መሎጊያዎቹንና ዕቃውን ሁሉ ። |
| ወማእከከ ምስለ መንበሩ ወመንጦላዕተ ዓፀድ ወአዕ | ፴፰ | መታጠቢያን ከነመቀመጫው የአደባባዩን መጋረጃ ምሰ |

ማዲሁ ወመከየዲሆን ።

፴፱ ወመከደኒ እንቀጸ ዓፀድ ወሐብላታቲሁ ወመቃግሪሁ ወመታክሊሁ ወኵሎ ንዋያተ ምግባረ ደብተራ ዘመርጡል ፤

፵ ወአልባሰ ቅድሳት ዘአሮን ወአልባሰ ደቂቁ ዘክህነቶሙ ወዘተርፉ አልባሳተ ለምግባረ ደብተራ፥ ወመክደንተ በዕድኒ ።

፵፩ በከመ ኵሉ ዘአዘዞ እግዚአብሔር ለሙሴ፥ ከማሁ ገብሩ ደቂቀ እስራኤል ኵሎ ሥርዓቶ ።

፵፪ ወርእየ ኵሎ ዘተገብረ ዘገብሩ ዘከመ አዘዞ እግዚአብሔር ከማሁ ተገብረ፥ ወባረኮሙ ሙሴ ።

ምዕራፍ ፵ ።

፩ ወተናገሮ እግዚአብሔር ለሙሴ ወይቤሎ አመ ርእሰ ሠርቀ ቀዳሚ ወርኅ ትትክላ ለደብተራ መርጡል ።

፪ ወታንብር ውስቴታ ታቦተ ዘስምዕ ወትክድና ለታቦት በመንጦላዕት ።

፫ ወታበውእ ማእደ ወትሠርዖ በሥርዓቱ ወታበውእ መራናተ ወትሠርዕ መኃትዊሃ ።

፭ ወታንብር ማዕጠንተ ዘወርቅ ቅድመ ታቦት ዘስምዕ ወታንብር መንጦላዕተ ኆኅተ ደብተራ ዘመርጡል ።

፮ ወታንብሮ ለምሥዋዕ ዘመሥዋዕት በቅድመ ኆኅተ ደብተራ ዘመርጡል ወታንብር ማእከከ ማእከለ ደብተራ ወማእከለ ምሥዋዕ፥ ወትወዲ ውስቴቱ ማየ።

፯ ወትትክል ዓፀደ ዓውዱ ወታንብር መክደኒ እንቀጸ በዐፀድ ።

፯ ወትነሥእ ቅብዐ ዘበቱ ይትቀብኡ ወትቀብኣ ለደብተራ ወለኵሉ ዘውስቴታ ወትቄድሳ ኪያሃ ወኵሉ ንዋያቲሃ ወትከውን ቅድስተ ።

፰ ወትቀብኦ ለምሥዋዕ ዘመሥዋዕት ወለኵሉ ንዋያቲሁ ወትቄድሶ ለምሥዋዕ ወይከውን ውእቱ ምሥዋዕ ቅዱሰ ቅዱሳን ወትቀብኦ ለማእከከ ወለመንበሩ፥ ወትቄድሶ ።

፱ ወታቀርቦሙ ለአሮን ወለደቂቁ ኀበ ኆኅተ ደብተራ ዘመርጡል ወተሐጽቦሙ በማይ ።

፲ ወታለብሶ ለአሮን አልባሰ ቅድሳት ወትቀብኦ ወትቄድሶ ወይከውነኒ ክህነ ።

፲፩ ወታቀርቦሙ ለደቂቁ ወታለብሶሙ አልባሲሆሙ ወትቀብኦሙ በከመ ቀባዕኮ አባሆሙ ወይከውኑኒ ክህናተ ።

፲፪ ወይከውኖሙ ዝንቱ ቅብዓት ዘክህነት ዘለዓለም ለትውልዶሙ ።

፲፫ ወገብረ ሙሴ ኵሎ ዘአዘዞ እግዚአብሔር ከማሁ ገብረ ።

፲፬ ወኮነ በቀዳሚ ወርኅ በካልእት ዓመት እምዘወጽኡ

ሰዎቹንና እግሮቻቸውን ።

የአደባባዩን ደጃፍ መጋረጃ ለሰንሰሎቶቹን አውታሮቹን ካስማዎቹን ለደብተራ ኦሪት የሚሆኑ ዕቃዎችን ሁሉ ።

በመቅደሱ ውስጥ ለማገልገል የተቀደሱትን የክህኑ የአሮንን ልብሶች በክህነት ሊያገለግሉት የልጆቹንም ልብሶች የቀሩትንም ለደብተራ ኦሪት ሥራ የሚሆኑ ልብሶችን ሌላውን የሚሸፍኑባቸውንም፥ ወደ ሙሴ አመጡ ።

እግዚአብሔር ሙሴን እንዳዘዘው ሁሉ የእስራኤል ልጆች ሥራውን ሁሉ እንዲሁ አደረጉ ።

ሙሴም የተሠራውን ሁሉ አየ፥ እነሆም እግዚአብሔር እንዳዘዘው እንዲሁ እንደተደረገ አይቶ ባረካቸው ።

ምዕራፍ ፵ ።

እግዚአብሔርም ሙሴን እንዲህ ብሎ ተናገረው፥ ከመጀመሪያው ወር በፊተኛው ቀን የመገናኛውን ድንኳን ትተክላለህ ። ዘፀ፥ ፲፪ ፪፥ ግብ፥ ሐዋ፥ ፯ ፵፬ ፵፭ ።

በርሷም ውስጥ የምስክሩን ታቦት ታኖራለህ ታቦቱንም በመጋረጃ ትጋርዳለህ ። ዘኊ፥ ፬ ፭ ።

ገበታውንም አግብተህ በርሱ ላይ የሚኖረውን ዕቃ ታሰናዳለህ መቅረዙንም አግብተህ ቀንዲሎቹን ትለኩሳለህ ።

በምስክሩም ታቦት ፊት የወርቅ ማዕጠንትን ታኖራለህ፥ በደብተራ ኦሪትም ደጃፍ ፊት መጋረጃውን ትጋርዳለህ ።

ለሚቃጠል መሥዋዕት የሚሆነውንም መሠውያ በመገናኛው ድንኳን በማደሪያው ደጅ ፊት ታኖረዋለህ፥ የመታጠቢያውንም ሰን በመገናኛው ድንኳንና በመሠውያው መካከል አኑረህ ውኃ ትጨምርበታለህ ።

በዙርያውም አደባባዩን ትተክላለህ፥ የአደባባዩንም (ወትተክል) ደጃፍ መጋረጃ ትዘረጋለህ ።

የሚቀቡትን ቅብዐ ቅዱስ ወስደህ ድንኳኑን በውስጧ ያለውንም ሁሉ ቀብ፥ እርሱንም ዕቃዎቹንም ሁሉ ትቀድሰዋለህ፥ ቅዱስም ይሆናል ። ዘፀ፥ ፴ ፳፫ - ፳፯ ።

ለሚቃጠል መሥዋዕት የሚሆነውንም መሠውያና ዕቃውንም ሁሉ ትቀብዋለህ፥ መሠውያውንም ትቀድሰዋለህ፥ መሠውያውም ቅዱስ ቅዱሳን ይሆናል፥ የመታጠቢያውን ሰን መቀመጫውንም ቀብተህ ቀድሰው ። ዘፀ፥ ፳፱ ፴፯።

አሮንንና ልጆቹን ወደ መገናኛው ድንኳን አቅርበህ በውኃ እጠባቸው ። ሌዋ፥ ፰ ፩ - ፲፫ ።

የተቀደሰውን ልብስ ለአሮን አልብሰው ቀብተህም ቀድሰው አገልጋይም ይሆነኛል ። ዘፀ፥ ፳፰ ፵፩ ።

ልጆቹንም አቅርበህ ልብሶቻቸውን አልብሳቸው፥ አባታቸውንም እንደ ቀባህ ቀባቸው፥ እነሱም አገልጋዮች ይሆኑኛል ። መዝ፥ ፻፴፫ ፪፥ ዕብ፥ ፯ ፳፫ ።

ይህም የክህነት ቅብዓት ለልጅ ልጆቻቸው ለዘለዓለም ይሆንላቸዋል ። ዘኊ፥ ፳፩ ፲፫ ፥ ዕብ፥ ፯ ፲፩ ።

ሙሴም እግዚአብሔር እንዳዘዘው ሁሉ እንዲሁ አደረገ ።

ከግብጽ አገር በወጡ በሁለተኛው ዓመት በመጀመ

| | | |
|---|---|---|
| እምድረ ግብጽ አመ ርእሰ ሠርቀ ወርኅ ተከልዋ ለደብተራ ፤ | | ርያው ወር ድንኳኒቱን ተከሏት ። |
| ወተከላ ሙሴ ለደብተራ ወአስተናበረ ምዕማዲሃ ወአቀመ አዕማዲሃ ወወደየ መናሥግቲሆን ። | ፲፭ | ሙሴ ድንኳኒቱን ተከላት ፤ ምዕማዶቿንም አኖረ ፤ ሳንቆቿን አቆመ ፤ መወርወሪያዎቹንም አገባባቸው ። |
| ወአቀመ አዕማዲሃ ወሰፍሐ አዕፃዲሃ ለደብተራ ወአንበረ ሠቃተ ዲበ ደብተራ ። | ፲፮ | ምሰሶዎቹን አቆመ ፤ የድንኳኑንም ፈርጅ ዘረጋ ፤ መደረቢያዎችንም በድንኳኑ ላይ አደረገ ። |
| ወአንበረ መክደኒ መልዕልተ ሠቅ ዘከመ አዘዘ እግዚአብሔር ለሙሴ ። | ፲፯ | እግዚአብሔርም ሙሴን እንዳዘዘው በመደረቢያው ላይ መሸፈኛውን አኖረ ። |
| ወነሥአን ሙሴ ለመጻሕፍተ ትእዛዝ ወወደዮን ውስተ ታቦት ወአንበሮን ለመሳውርት ውስተ አውታፉተ ታቦት ። | ፲፰ | ሙሴ የትእዛዛቱን መጻሕፍትን ወስዶ በታቦቱ ውስጥ አገባቸው ፤ መሎጊያዎቹንም በታቦቱ ቀለበቶች አገባቸው ። |
| ወአንበሮ ለምስሐል መልዕልተ ታቦት ወአብአ ለታቦት ውስተ ደብተራ ። | ፲፱ | የሥርየት መክደኛውንም በታቦቱ ላይ አኖረው ፤ ታቦቱንም ወደ ድንኳኑ ውስጥ አገባት ። |
| ወወደየ መክደና መንጦላዕተ ወሠወራ ለታቦተ መርጡል ዘከመ አዘዘ እግዚአብሔር ለሙሴ ። | ፳ | እግ ፡ አብሔር ሙሴን እንዳዘዘው መክደኛዋን መጋረጃ አድርጎ ታቦቱን ሸፈናት ። ዘፀ ፡ ፴፩ ፲፰ ። |
| ወአንበሮ ለማእድ ውስተ ደብተራ ዘመርጡል መንገለ ገቦሃ ዘመስዕ ለደብተራ እምአፍአሁ ለመንጦላዕት ። | ፳፩ | ገበታውን በመገናኛው ድንኳን ውስጥ ከመጋረጃው ውጭ በደብተራ ኦሪት በሰሜን በኩል አኖረው ። |
| ወሠርዐ ውስቴታ ኅብስተ ቍርባን ቅድመ እግዚአብሔር ዘከመ አዘዘ እግዚአብሔር ለሙሴ ። | ፳፪ | እግዚአብሔር ሙሴን እንዳዘዘው የቍርባኑን ኅብስት በውስጧ በእግዚአብሔር ፊት አሰናዳ ። ዘፀ ፡ ፳፭ ፴፯ ። |
| ወአንበራ ለመራናት ውስተ ደብተራ መርጡል አንጻረ ማእድ መንገለ አዜብ ለደብተራ ። | ፳፫ | መቅረዙንም በመገናኛው ድንኳን ውስጥ ፊት ለፊት በድንኳኑ በስተ ደቡብ በኩል አኖረው ። |
| ወሠርዐ መኃትዊሃ ቅድመ እግዚአብሔር በከመ አዘዘ እግዚአብሔር ለሙሴ ። | ፳፬ | እግዚአብሔር ሙሴን እንዳዘዘው ቀንዲሎቹን በእግዚአብሔር ፊት አዘጋጀ ። ዘፀ ፡ ፴ ፯ ። |
| ወአንበረ ማዕጠንተ ዘወርቅ ውስተ ደብተራ ዘመርጡል ቅድመ መንጦላዕት ። | ፳፭ | የወርቁንም ማዕጠንት በደብተራ ኦሪት ውስጥ ከመጋረጃው ፊት አኖረ ። ዘፀ ፡ ፳፯ ፴፯ ። |
| ወዐጠነ ውስቴቱ ዕጣነ ዘኀብረ ዘከመ አዘዘ እግዚአብሔር ለሙሴ ። | ፳፮ | እግዚአብሔር ሙሴን እንዳዘዘው ያቀረበውን ዕጣን በውስጥ አጠነበት ። ዘፀ ፡ ፳፱ ፴፰ ። |
| ወአንበሮ ለመክደኒ ኆኅተ ደብተራ ወለምሥዋዐ ዘመሥዋዕት አንበሮ ኀበ ኆኅተ ደብተራ ። | ፳፯ | በድንኳኑም ደጃፍ ፊት መጋረጃውን ዘረጋ ፤ ለሚቃጠል መሥዋዕት የሚሆነውን መሠውያ በደብተራ ኦሪት ደጃፍ ፊት አኖረው ። |
| ወአዕረገ ላዕሌሁ መሥዋዕተ ወቍርባነ ዘከመ አዘዘ እግዚአብሔር ለሙሴ ወአንበሮ ለማሕከክ ማእከለ ደብተራ ወማእከለ ምሥዋዕ ። | ፳፰ | እግዚአብሔርም ሙሴን እንዳዘዘው በላዩ ላይ የሚቃጠለውን መሥዋዕት ሠዋበት መታጠቢያውንም በድንኳኑና በመሠውያው መካከል አኖረው ። |
| ወወደየ ውስቴቱ ማየ ከመ ይትሐፀቡ ቦቱ አሮን ወደቂቁ እደዊሆሙ ወእገሪሆሙ ሶበ ይበውኡ ውስተ ደብተራ ወሶበ ይቀርቡ ኀበ ምሥዋዕ ዘከመ አዘዘ እግዚአብሔር ለሙሴ ። | ፳፱ | እግዚአብሔር ሙሴን እንዳዘዘው አሮንና ልጆቹ ወደ ደብተራ ኦሪት በሚገቡበትና ወደ መሠውያው በሚቀርቡበት ጊዜ እጆቻቸውንና እግሮቻቸውን በርሱ ይታጠቡ ዘንድ ውኃን ጨመረበት ። ዘፀ ፡ ፴ ፲፱ ። |
| ወአቀመ ዐፀደ በዐውደ ደብተራ ወምሥዋዕ ወአንበሮ ለምክዳኑ አንቀጸ ዘዐፀድ በከመ አዘዘ እግዚአብሔር ለሙሴ | ፴ | ሙሴም እግዚአብሔር እንዳዘዘው በድንኳኑና በመሠውያው ዙርያ አደባባዩን አቆመ ፤ (ተከለ) በአደባባዩም ደጃፍ መጋረጃ ዘረጋበት ። |
| ወፈጸመ ሙሴ ኵሎ ግብሮ ወከደና ደመና ለደብተራ መርጡል ወስብሐተ እግዚአብሔር ተመልአት ደብተራ ። | ፴፩ | ሙሴ ሥራውን ሁሉ ሠርቶ እንደፈጸመ ደብተራ ኦሪትን የእግዚአብሔር ብርሃን ወርዶ ሸፈናት ፤ ደብተራ ኦሪትም የእግዚአብሔር ክብር (ብርሃን) ተመላች ። |
| ወስእነ ሙሴ በዊአ ውስተ ደብተራ መርጡል እስመ ጸለላ ደመና ወስብሐተ እግዚአብሔር ተመልአት ደብተራ ። | ፴፪ | ደብተራ ኦሪት ደመና ብርሃን ጋርዷታልና የእግዚአብሔርንም ብርሃን ተመልታለችና ሙሴ ወደ ደብተራ ኦሪት መግባት ተሳነው ። ዘኍ ፡ ፲ ፲፩ ፡ ነገ ፡ ፰ ፲፱ ። |
| ወእምከመ ሰሰለ ደመና እምላዕለ ደብተራ ይግዕዙ ደቂቀ እስራኤል በበንገዶሙ ። | ፴፫ | የደመናው ብርሃንም ከደብተራ ኦሪት በተነሣ ጊዜ የእስራኤል ልጆች በየነገዳቸው ይጓዙ ነበር ። |

፴፯ ወእመሰ ኢ.ሰሰለ ደመና ኢ.ይግዕዙ እስከ አመ ይሴስል ደመና እስመ ደመና ይነብር ላዕለ ደብተራ መንጦት ።

ደመናው ብርሃን ተነሥቶ ካልሄደ ግን ደመናው እስ ኪነሣላቸው ድረስ አይጓዙም ነበር ፥ ደመናው ቀን በድ ንኳኑ ላይ ነበርና ። ዘፀ፡ ፲፫ ፳፩ ።

፴፰ ወእሳተ ይከውን ላዕሌሃ ሌሊተ ቅድመ ኵሉ እስራ ኤል በኵለሄ ኀበ ግዕዙ ።

ሌሊትም እስራኤል ሁሉ በተጓዙበት በታ ፊት በድ ንኳኑ ላይ እሳት ሁኖ ስፍሮበት ይውል ነበርና ።



ተፈጸመ ኦሪት ዘፀአት፤
ወለእግዚአብሔር ክብር ወስብሐት፤
አሜን ።

የእስራኤልን መውጣት የሚናገር መጽሐፍ ተፈጸመ
ለእግዚአብሔር ክብርና ምስጋና ለዘለዓለሙ
አሜን ።

## ኦሪት ዘሌዋውያን

ስለ እስራኤል መውጣት ነገር ተናግሮ ፥ የደብረ ሲናን የ፲ቱ ቃላትን የደብተራ ኦሪትን ሲገልጽ መጥቶ ነበርና ፥ አሁን ደግሞ የክህናቱንና የመሥዋዕቱን ሕግና ወግ ለመናገር ያመጣዋል ። የሌዋውያንን የክህናቱን ሕግና ወግ የሚናገር መጽሐፍ ይህ ነው ።

አባቶቻችን ሠለስቱ ምእት ሊቃውንት ለመጻሕፍት ሁሉ አርእስት ሲሰጡ ለዚህም ይህን አርእስት ሰጥተውታል ። እርሱ ግን ነገሩን "ወጸውዖ እግዚአብሔር ለሙሴ„ ብሎ ይጀምራል ።

# ኦሪት ዘሌዋውያን

ምዕራፍ ፩ ።

፩ ወጸውዖ እግዚአብሔር ለሙሴ ወተናገሮ እምውስተ ደብተራ ዘመርጡል ።
፪ ወይቤሎ በሎሙ ለደቂቀ እስራኤል ወአይድዖሙ እመብእሲ እምኔክሙ ዘአብአ መባአ ለእግዚአብሔር እምእንስሳ ወእምአልሕምት ወእምአባግዕ ታበውኡ መባአክሙ።
፫ ለእመ ለመዋዕ መባኡ እምአልሕምት ተባዕተ ንጹሐ ያመጽእ ኀበ ኆኅተ ደብተራ ዘመርጡል ወያበውኦ ሥሙረ ቅድመ እግዚአብሔር ።
፬ ወያንብር እዴሁ ላዕለ ርእሱ ለገብሩ ላሕም ዘአምጽአ ለመዋዕት ከመ ይሠረይ ወያስተሥሪ ሎቱ በእንቲአሁ ።
፭ ወይጠብሕዎ ለውእቱ ላሕም ቅድመ እግዚአብሔር ወያመጽኡ ደቂቀ አሮን ደሞ ለሊሆሙ ካህናት ወይክዕውዎ ላዕለ ምሥዋዕ ዓውዶ ኀበ ኆኅተ ደብተራ ዘመርጡል ።
፮ ወይጠብሕዎ ወይፈልጡ መለያልይሁ ዘዘዚአሁ ።

፯ ወይወድዩ እሳተ ደቂቀ አሮን ካህናት ላዕለ ምሥዋዕ ወይሬሥዩ ዕፀወ እሳት ።
፰ ወይሬሥዩ ደቂቀ አሮን ካህናት ዝክቱ ዘገመዱ ርእሶ ወስብሖ ላዕለ ዕፀው ዘላዕለ እሳት ዘዲበ ምሥዋዕ ።

፱ ወንዋየ ውስጡ ወእገሪሁ የሐጽቡ በማይ፤ ወይወዲ ካህን ኵሎ ዲበ ምሥዋዕ መሥዋዕት ውእቱ ወቍርባን ዘመዓዛ ሠናይ ለእግዚአብሔር ።
፲ ወእመሰ እምአባግዕ ውእቱ መባኡ ለእግዚአብሔር እመኒ በግዕ ወእመኒ ማሕስእ ለመዋዕ ተባዕተ ንጹሐ ያመጽእ ።
፲፩ ወይጠብሕዎ በገቦ ምሥዋዕ ዘመንገለ መስዕ ቅድመ እግዚአብሔር ወይክዕዉ ደሞ ደቂቀ አሮን ካህናት ላዕለ ምሥዋዕ በዓውዱ ።
፲፪ ወይመትርዎ ካህናት በበመለያልይሁ ርእሶ ወስብሖ ወይሬሥይዎ ላዕለ ዕፀው ዘዲበ እሳት ዘላዕለ ምሥዋዕ ።

፲፫ ወንዋየ ውስጡ ወእገሪሁ የሐጽቡ በማይ ወያመጽእ ካህን ኵሎ ወያነብሮ ላዕለ ምሥዋዕ ለቍርባን መሥዋዕት ውእቱ ወመዓዛ ሠናይ ለእግዚአብሔር ።

፲፬ ወእመሰ እምአዕዋፍ ያበውዕ መሥዋዕቶ ቍርባኖ ለእ

ምዕራፍ ፩ ።

እግዚአብሔር ከደብተራ ኦሪት ውስጥ ሆኖ ሙሴን ጠርቶ እንዲህ ሲል ተነጋገረው ። ዘኍ፣ ፩ ፩ · ፱ ።
ከናንተ ወገን ለእግዚአብሔር መባውን የሚያገባ ሰው ቢኖር ከከብት ወገን ከላሞች ከበጎች መባቻሁን አቅርቡ፣ ብለህ ለእስራኤል ልጆች ንገራቸው አለው ።
የሚያቀርቡት መባ ለመሥዋዕት ከሆነ ከላም ወገን ነውር የሌለበትን ተባቱን በእግዚአብሔር ፊት ወዶ እንዲቀበለው አድርጎ ወደ ደብተራ ኦሪት ደጃፍ ያምጣው ።
ሊሠዋውም ያመጣው ሰው በላሙ ራስ ላይ እጁን ይጫንበት ወዶ ተቀብሎ ኃጢአቱን ያስተሠርይለት ዘንድ ።
ላሙንም በእግዚአብሔር ፊት ይረዱት፣ የአሮንም ልጆች ካህናቱ ራሳቸው ደሙን በደብተራ ኦሪት ደጅ ባለ በምሥዋዑ ዙርያ ይረብርቡት ። ዕብ፣ ፲ ፲፩ ።

አርደው አወራርደውም ብልቱን በየዘርፉ ለያይተው ይቍረጡት ። ዘሌ፣ ፳፯ ፲፪፣ ዘሌ፣ ፰ ፳ ።
የአሮን ልጆች ካህናቱም ከመሠውያው ላይ እሳት እንድደው ዕንጨቱን በእሳቱ ላይ ይረብርቡት ።
የአሮን ልጆች ካህናት አርደው ያወራረዱትን ሥጋ ራሱንም ስቡንም በመሠውያው በነደደው እሳት ባለው ዕንጨት ላይ ይደርድሩት ። ዘሌ፣ ፯ ፲፪፣ ፰ ፳ ።
ሆድ ዕቃውንና እግሮቹን በውኃ አጥበው ካህኑ ሁሉንም በምሥዋዑ ላይ ያድርገው (ያሳርገው)፣ ይኸውም እግዚአብሔር ወዶ የሚቀበለው መሥዋዕትና ቍርባን ነው ።
ለእግዚአብሔር የሚቀርበው መባ ከበጎች ወገን ቢሆን ግን በግም ቢሆን ፍየልም ቢሆን፣ ለመሥዋዕት ነውር የሌለበትን ተባት ያምጡ፣ (ያቅርቡ) ።
በእግዚአብሔር ፊት በምሥዋዑ አጠገብ በሰሜን በኩል ይረዱት፣ የአሮን ልጆች ካህናትም ደሙን ተቀብለው በመሠውያው ላይ በዙርያው ይርጩት ።
ካህናቱ ራሱንና ስቡንም ብልት ብልቱን ቈራርጠው ለይተው በመሠውያው አጠገብ በነደደው እሳት አጠገብ ባለው ዕንጨት ላይ ይረብርቡት ። ቍ፣ ፰ ።
ሆድ ዕቃውንና እግሮቹን (ሰኰናውን) ግን በውኃ ይጠቡት፣ ካህኑም ሥጋውን ሁሉን አምጥቶ በምሥዋዑ ላይ ያድርገው (ያቃጥለው)፣ እግዚአብሔር ወዶ የሚቀበለው መሥዋዕት ነውና ። ዘሌ፣ ፭ ፯፣ ፲፪ ፰ ።
ለእግዚአብሔር የሚያቀርብ መሥዋዕት ከአዕዋፍ

ግዚአብሔር ያመጽእ እመ እከ እማዕነቅ ወእመ እኮ እም ርግብ ቍርባኖ፤ ያመጽእ ካህን ኀበ ምሥዋዕ ።

ወገን ቢሆን ግን ከዋኖስ ወይም ከርግብ ካህኑ ቍርባኑን ወደ መሠውያው ያምጣ ።

፲፭ ወይመትር ክሳዶ ወያነብሮ ላዕሌ ምሥዋዕ ወያንጸፈጽፍ ደሞ ኀበ መንበረ ምሥዋዕ ።

አንገቱን ገዝግዞ በመሠውያው ያኑረው (ያቃጥለው) ደሙንም ከመሠውያው አግር ያንጠፍጥፈው ።

፲፮ ወያሴስል ንዋየ ውስጡ ምስለ ፀጕሩ ወያነብሮ በገበ ምሥዋዕ ዘመንገለ ጽባሒሁ ኀበ መንበረ ሐመድ ።

ሆድ ዕቃውንም ከጠጕሩ ጋር አመዱ በሚፈስበት በታ በመሠውያው አጠገብ በስተምሥራቅ በኩል ያፍስ ሰው (አውጥቶ ይጣለው) ። ዘሌ፣ ፱ ፲፫ ።

፲፯ ወይሰብሮ ክነፊሁ ወኢይመትሮ፤ ወያነብሮ ካህን ላዕለ ምሥዋዕ በዲበ ዕፀው ዘላዕለ እሳት ።

ክስክሳዎቹን (ክንፎቹን) ይሰብረው፤ ቈርጦ አይጣለው (አይለየው) ካህኑም በምሥዋዑ ላይ በእሳቱ በለው ዕንጨት ላይ አድርጎ ያቃጥለው ።

፲፰ ቍርባን ውእቱ ዘመሥዋዕት ወመዓዛ ሠናይ ለእግዚ አብሔር ።

ለእግዚአብሔር በጎ መዓዛ ያለው ወዶ የሚቀበለው መሥዋዕት ነውና ። ዘፍ፡ ፲፭ ፲ ።

## ምዕራፍ ፪ ።

፩ ወእመሰ ህየንተ ነፍስ ቍርባነ ወመሥዋዕተ ለእግዚአ ብሔር ያመጽእ ሥንዳሌ ይኩን ቍርባኑ፤ ወይክዑ ላዕሌሁ ቅብዐ ወይወዲ ዲቤሁ ስኂነ ።

ማናቸውም ሰው ስለ ሰውነቱ ለእግዝ አብሔር የእኽል ቍርባን መሥዋዕት ቢያመጣ (ቢያቀርብ) ልጦ ጕሬዶ የወጣለት ሥንዴ ልዝብ ዱቄት ይሁን፤ ዘይት ያፍስስበት ነጭ ዕጣን ያድርግበት ። ዘኍ፣ ፲፭ ፬ ።

፪ ወይወስዶ ኀበ ደቂቀ አሮን ካህን ወይዘግን እምኔሁ ካህን ምልአ ሕፍኑ እምሥንዳሌ ምስለ ቅብዑ ወኵሉ ስኂኑ ወይወድዮ ለተዝካር ላዕለ ምሥዋዕ፤ መሥዋዕት ውእቱ ዘመዓዛ ሠናይ ለእግዚአብሔር ።

ወደ ክህናቱ ወደ አሮን ልጆች ይውሰደው ካህኑም በዘይት ከታሸው ዱቄት እጅ ሙሉ ዘግኖ ዕጣኑንም ወስዶ መታሰቢያ ሊሆን በምሥዋው ላይ ያቃጥለው እግዚአብሔር ወዶ የሚቀበለው ያማረ መሥዋዕት ነውና።

፫ ወዘተርፈ እመሥዋዕት ለአሮን ወለደቂቁ ቅዱስ ለቅዱሳን እመሥዋዕቱ ለእግዚአብሔር ።

ከመሥዋዕቱ ጢሰለት የተረፈውም ለአሮንና ለልጆቹ ይሁን፤ ከእግዚአብሔር መሥዋዕት ጢዕለት የተረፈው ቅዱስ ለቅዱሳን ነውና ። ዘፀ ፳፱ ፴፯ ፤ ዘኍ፣ ፲፰ ፱ ።

፬ ወእመሰ አብእከ ቍርባነ ለመሥዋዕት ብሑለ በእቶን ግብርት ሥንዳሌ ናእት ልዉስ በቅብዕ ።

በእሳት የበሰለውን ቍርባን አድርገህ ለመሥዋዕት ብታቀርብ በዘይት የተለወሰ የሥንዴ ዳቦ (ቂጣ) ይሁን ።

፭ ወእመ መሥዋዕተ ቴጉን ቍርባንከ ሥንዳሌ ልዉስ በቅብዕ ወናእተ ይኩን ወትፈትቶ ወትክዑ ላዕሌሁ ቅብዐ ።

ቍርባንህ በምጣድ የተጋገረ ቢሆን ግን በዘይት የተለወሰ ከመልክም ሥንዴ ዱቄት ያልቦካ ቂጣ ይሁን፤ ቈርሰህም ዘይት አፍስስበት ።

፮ ወለእመ ብሱል በመቅጹት መሥዋዕትከ ሥንዳሌ በቅብዕ ይትገበር ።

መሥዋዕትህ በምንቸት የተቀቀለ (የተገነፋ) ነገር ቢሆን በዘይት የተለወሰ የሥንዴ ዱቄት ይሁን ።

፯ ወታመጽእ መሥዋዕተ ዘገበርከ እምዝንቱ ለእግዚአብሔር ኀበ ካህን፤ ወያቀርቦ ካህን ኀበ ምሥዋዕ ።

ከዚህ ሁሉ ያደረግኸውን መሥዋዕትህን ለእግዚአብሔር አምጥተህ ወደ ካህኑ አቅርበው ካህኑም ወደ ምሥዋው ያቅርበው ።

፰ ወይነሥእ ካህን እመሥዋዕት ለተዝካር ወይወድዮ ላዕለ ምሥዋዕ መሥዋዕት ውእቱ ወመዓዛ ሠናይ ለእግዚ አብሔር ።

ካህኑም መታሰቢያ ሊሆን ከመሥዋዕቱ አምጥቶ በመሠውያው ላይ ያቃጥለው በጎ መዓዛ ያለው ሁኖ ለእግዚ አብሔር የሚቀርብ መሥዋዕት ነውና ። ዘፍ፡ ፳፱ ፲፰ ።

፱ ወዘተርፈ እመሥዋዕት ለአሮን ወለደቂቁ ቅዱስ ለቅዱሳን እመሥዋዕቱ ለእግዚአብሔር ።

ለእግዚአብሔር ከቀረበው መሥዋዕት የቀረው ከከበሩ ለተከበሩት ለአሮን ልጆች ይሁን ። ዘፀ፣ ፳፱ ፴፯ ።

፲ ኵሉ ዘታመጽኡ ለሠዊዕ ለእግዚአብሔር ኢትግበሩ ብኍዓ እምኵሉ ብኍዕ ወእምኵሉ መዓር ኢታምጽኡ ለሠዊዕ ለእግዚአብሔር ለቍርባን ።

ለእግዚአብሔር ብላችሁ የምታመጡትን መሥዋዕት ሁሉ መጻጻ አታድርጉት፤ መጻጻ ካለበት ነገር ሁሉ ከማርም ሁሉ ቍርባን ሊሆን ለእግዚአብሔር አታምጡ ።

፲፩ ወበሕቱ ለዓሥራት ታበውኡ እምኔሁ ለእግዚአብሔር ለመሥዋዕትሰ ኢትሠውዑ እምኔሁ ለመዓዛ ሠናይ ለእግዚ አብሔር ።

ብቻ ለእግዚአብሔር ከምታቀርቡት ከሱ (ከማር) ከሥር አንዱን ታገባላችሁ፤ በምሥዋው ላይ ለእግዚአብሔር በጎ ሽታ ሊሆን ከርሱ አትሠዉ ። ዘፀ፣ ፳፪ ፳፱ ።

፲፪ ወኵሉ ቍርባነ መሥዋዕትክሙ በጼው ይትገበር ወኢይትኃደግ ጼው እንዘ ትሠውዑ ለእግዚአብሔር ውስተ ኵሉ ቍርባንክሙ ትወድዩ ጼወ ።

የመሥዋዕታችሁ ቍርባን ሁሉ በጨው ይጣፈጥ ለእግዚአብሔር ስትሠዉ ጨው አይቅር፤ በምታቀርቡት ቍርባናችሁ ሁሉ ጨው ጨምሩበት ። ማር፣ ፱ ፵፱ ።

| | | |
|---|---|---|
| ወእመሰ አበእከ መሥዋዕተ እምቀዳሚ እክልከ ለእግዚአብሔር ሐዲሰ ቅልወ ንጹሐ ወልቱመ ታበውእ መሥዋዕተ እምቀዳሚ እክልከ ። | ፲፫ | ሙጀ ሙርያ ከደረሰው እኽልህ ለእግዚአብሔር መሥዋዕት ብታቀርብ ግን ፤ አዲስ የተቈላ የተፈተገ ፤ የተለቀሙውን መጀመርያ ከደረሰው እኽልህ አቅርብ ። |
| ወትከዑ በላዕሌሁ ቅብዐ ወትወዲ ላዕሌሁ ስኂነ ። | ፲፬ | በላዩ ላይ ዘይት አፍስስበት ፤ ቍንዶ በርበሬም ጨምርበት ። |
| ወያበውእ ካህን ለውእቱ እክል ምስለ ቅብዑ ወኵሉ ስኂኑ ለተዝካር መሥዋዕት ውእቱ ለእግዚአብሔር ። | ፲፭ | ካህኑም ያንን እህል ከዘይቱና ከቍንዶ በርበሬው ጋር ለመታሰቢያ ያግባው ለእግዚአብሔር የሚጤስ መሥዋዕት ነውና ። |
| ምዕራፍ ፫ ። | | ምዕራፍ ፫ ። |
| ወእመሰ መሥዋዕተ መድኃኒት ውእቱ ቍርባኑ ለእግዚአብሔር ለእመ እምአልሕምት አምጽአ እመኒ ተባዕተ ወእመኒ አንስተ ንጹሐ ለያምጽእ ቅድመ እግዚአብሔር ። | ፩ | ለእግዚአብሔር የሚቀርበው ቍርባን የደኅንነት መሥዋዕት ሲሆን ከላሞች ወገን ተባትም ቢሆን እንስትም ቢሆን ንጹሕ የሆነውን በእግዚአብሔር ፊት ያቅርብ ። |
| ወይወዲ እዴሁ ላዕለ ርእሱ ወይጠብሕዎ ኀበ ኆኅተ ደብተራ ዘመርጡል ወይክዕዉ ደሞ ደቂቀ አሮን ካህናት ላዕለ ምሥዋዕ በዓውዱ ። | ፪ | የሚሠዋውም ሰው በሚሠዋው መሥዋዕቱ ላይ እጁን ይጫንበት ፤ በደብተራ ኦሪት ደጃፍ ይረዱት (ይሠዉት) የአሮን ልጆች ካህናትም ደሙን ተቀብለው በምሥዋው ዙርያ ይረጭበ፤ ቡት (ይርጩት) ። ዘሌ፤ ፩ ፱ ። |
| ወያበውኡ እመሥዋዕተ መድኃኒት ቍርባነ ለእግዚአብሔር ስብሐ ዘይገለብብ ከርሦ ወኵሎ ስብሐ ዘውስተ ከርሡ ። | ፫ | ድኅነት ከሚደረግበት መሥዋዕት ሆዱን የሚሸፍነውን ስብ በሆዱም ውስጥ ያለውን ሁሉ ለእግዚአብሔር ቍርባን አድርገው ያምጡ ። ዘሌ፤ ፲፰ ፱፤ ዘፀ፤ ፳፱ ፲፫ ። |
| ወክልኤሆን ኵልያቶ ወስብሐ ዘላዕሌሆን ዘውስተ ጸራዊቱ ወከብዶ እንተ ትንእስ ምስለ ኵልያቲሁ ያመጽኡ ። | ፬ | ሁለቱንም ኵላሊቱ በርሳቸው ላይ ያለውን ስብ በጭቅናው (በሰብራደው) ላይ ያለውን ስብ፤ ሰምሰም ጉበቱን ከሁለት ኵላሊቶቹ ጋራ ያቅርቡ ። |
| ወያበውኡ ደቂቀ አሮን ላዕለ ምሥዋዕ ዲበ ዕፀው ዘላዕለ እሳት መሥዋዕት ውእቱ ወመዓዛ ሠናይ ለእግዚአብሔር ። | ፭ | የአሮንም ልጆች ከመሠውያው እሳት በለው ዕንጨት ላይ ያኑሩ (ያቃጥሉት) በጎ መዓዛ ሲሆን ለእግዚአብሔር የሚጤስ መሥዋዕት ነውና ። ዘፀ፤ ፳፱ ፲፫ ። |
| ወእመሰ እምአባግዕ ቍርባኑ ወመሥዋዕተ መድኃኒቱ ለእግዚአብሔር እመኒ ተባዕተ ወእመኒ አንስተ ንጹሐ ያመጽእ ። | ፮ | ለእግዚአብሔርም የደኅንነት መሥዋዕት አድርጎ የሚያቀርበው ቍርባኑ ከበጎች ወገን ቢሆን፤ ተባት ቢሆን እንስትም ቢሆን፤ ነውር የሌለበት ንጹሕ ያቅርብ ። |
| ወእመሰ ማሕስአ በግዕ ቍርባኑ ያመጽእ ቅድመ እግዚአብሔር ወይወዲ እዴሁ ላዕለ ርእሰ ቍርባኑ ። | ፯ | ቍርባኑ የበግ ጠቦትም ቢሆን ፤ በእግዚአብሔር ፊት አምጥቶ እጁን በሚሠዋው መሥዋዕት ራስ ላይ ያኑር ። |
| ወይጠብሕ ኀበ ኆኅተ ደብተራ ዘመርጡል ወይክዕዉ ደቂቀ አሮን ካህናት ደሞ ላዕለ ምሥዋዕ በዓውዱ ። | ፰ | በደብተራ ኦሪት ደጃፍም ይሠዋው ፤ የአሮን ልጆች ካህናትም ደሙን ተቀብለው በምሥዋው ዙርያ ይርጩት (ይረብርቡት) ። |
| ወይነሥእ እመሥዋዕተ መድኃኒት ቍርባነ ለእግዚአብሔር ስብሐ ወሐቌሁ ፍጹመ ምስለ ስመጢሁ ይመትሮ ወኵሎ ስብሐ ዘይገለብብ ከርሦ ወኵሎ ስብሐ ዘውስተ ከርሡ ። | ፱ | ደኅንነት ከሚገኝበትም መሥዋዕት ለእግዚአብሔር ቍርባን አድርጎ ቢያቀርብ ስቡን ዳሌውን ከሽንጡ ጋር ይለየው ፤ ሆድ ዕቃውን (ፈርሱን) የሚሸፍነውን ስቡን ሁሉ ፈቅቆ ይለየው ። ዘሌ፤ ፱ ፲፱፤ ዘፀ፤ ፳፱ ፳፪ ። |
| ወክልኤሆን ኵልያቲሁ ወስብሐ ዘዐራዊቱ ወከብዶ እንተ ትንእስ ምስለ ኵልያቲሁ ይመትሮ ወይወድዮ ካህን ላዕለ ምሥዋዕ ቍርባኑ ውእቱ ለእግዚአብሔር ። | ፲ | ሁለቱን ኵላሊቱ በጭቅናው (በሰብራደው) ያለውን ስቡን ግልገል ጉበቱን ከሁለት ኵላሊቱ ጋር ፈቅቆ ይለየው ፤ ካህኑ በምሥዋው ላይ ያጢሰው የእግዚአብሔር ቍርባን ነውና ። |
| ወእመሰ እምአጣሊ ቍርባኑ ለእግዚአብሔር ያመጽእ ቅድመ እግዚአብሔር ወይወዲ እዴሁ ላዕለ ርእሱ ። | ፲፩ | ለእግዚአብሔር የሚያቀርበው ቍርባን ከፍየል ወገን ቢሆን በእግዚአብሔር ፊት ያቅርበው ። ሕዝ፤ ሟ፱ ፯ ። |
| ወይጠብሕዎ ኀበ ኆኅተ ደብተራ ዘመርጡል ወይክዕዉ ደሞ ደቂቀ አሮን ላዕለ ምሥዋዕ በዓውዱ ። | ፲፪ | በደብተራ ኦሪት ደጃፍ የአሮን ልጆች ካህናትም ደሙን ተቀብለው በመሠውያው ዙርያ ይርጩት ። |
| ወይነሥእ እምኔሁ ቍርባነ ለእግዚአብሔር ስብሐ ዘይገለብብ ለከርሡ ፤ ወኵሎ ስብሐ ዘውስተ ከርሡ ። | ፲፫ | ከተሠዋው መሥዋዕት ለእግዚአብሔር የሚያቀርበው ሆድ ዕቃውን በሆድ ዕቃው በፈርሱ በአንጀቱ ያለውን ስብ ሁሉ ። |

፲፬ ወክልኤሆን ኵልያቲሁ ወኵሎ ስብሐ ዘላዕሌሆን ወዘ ጸራዊቱ ወከብዶ እንተ ትንእስ ምስለ ኵልያቲሁ ይመትሮ።

ሁለቱ ኵላሊቱን በኵላሊቱ ላይ ያለውን ስብ (ሞራ) በጭቅናው ውስጥ ያለውን ስብ ለምለም ጉበቱን ከሁለቱ ኵላሊቱ ጋራ ይህን ሁሉ አምጥቶ ያጢሰው ።

፲፭ ወያነብሮ ካህን ላዕለ ምሥዋዕ፣ መሥዋዕት ውእቱ ወመዓዛ ሠናይ ለእግዚአብሔር ።

ለእግዚአብሔር በጎ መሥዋዕት ሁኖ የሚቀርብ ነውና ካህኑ ቀቅሎ በምሥዋው ላይ ያኑረው ።

፲፮ ወኵሉ ስብሕ ለእግዚአብሔር ሕግ ዘለዓለም ውእቱ በኵሉ መዋዕሊክሙ ።

ለእግዚአብሔር የምታቀርቡት ስብ ሁሉ በዘመናችሁ ሁሉ የዘለዓለም ሕግ ነውና ።

፲፯ በኵለሄ በኀበ ትነብሩ ኵሎ ስብሐ ወኵሎ ደመ ኢትብልዑ ።

በምትኖሩበት (በየሀገራችሁ) ሁሉ ስቡን ሁሉ፣ ደሙንም ሁሉ አትብሉ ።

ምዕራፍ ፬ ።

ምዕራፍ ፬ ።

፩ ወተናገሮ እግዚአብሔር ለሙሴ ወይቤሎ ንግሮሙ ለደቂቀ እስራኤል ።

እግዚአብሔር ሙሴን ተናገረው ለእስራኤልም ልጆች እንዲህ ብለህ ንገራቸው አለው ።

፪ ወበሎሙ ነፍስ ለእመ አበሰት እምኵሉ ትእዛዘ እግዚአብሔር በኢያእምሮ ዘኢይከውን ለገቢር ወገብረት አሐተ እምኔሁ ።

ማንኛይቱም ሰውነት (ነፍስ) በለማወቅ ከእግዚአብሔር ትእዛዝ ወጥታ ሊሠሩዋት የማትገባውን ሥርታ ብትበድል አትሥሩ ካለው አንዲቱን ብትሠራ ። ዘኍ፣ ፲፭ ፳፪ ።

፫ ወእመኒ ሊቀ ካህናት ዘቅቡዕ አበሰ እምሕዝብ ያመጽእ ህየንተ አበሳሁ ዘአበሰ ላሕመ ንጹሐ እምአልሕምት ለእግዚአብሔር በእንተ ኃጢአቱ ።

ከሕዝቡ ተመርጦ የተሾመው የካህናቱ አለቃም ቢበድል ስለ ሠራው ኃጢአት ከላሞች ወገን መርጦ ነውር የሌለበትን ንጹሕ በሬ ለእግዚአብሔር ያቅርብ ።

፬ ወያመጽእ ለውእቱ ላሕም ኀበ ኆኅተ ደብተራ ዘመርጡል ቅድመ እግዚአብሔር፤ ወይወዲ እዴሁ ላዕለ ርእሰ ላሕም፣ ወይጠብሖ ለውእቱ ላሕም ቅድመ እግዚአብሔር ።

ያንንም በሬ በእግዚአብሔር ፊት ወደ ደብተራ ኦሪት ያምጣው እጁንም በላሙ ራስ ላይ ያኑር ያንንም በሬ በእግዚአብሔር ፊት ይሠዋው ። ምዕ፡ ፩ ፭ ።

፭ ወይነሥእ ካህን ዘቅቡዕ ወፍጹም በእዴሁ እምደሙ ለውእቱ ላሕም፣ ወያበውእ ውስተ ደብተራ ዘመርጡል ።

ተቀብቶ የተሾመውም ካህን የበሬውን ደም በእጁ ተቀብሎ ወደ ደብተራ ኦሪት ያግባው ። ዘኍ፣ ፲፱ ፬ ።

፮ ወይጠምዕ አፃብዒሁ ውስተ ደሙ ወይነዝኀ እምውእቱ ደም ስብዕ ቅድመ እግዚአብሔር ላዕለ መንጦላዕተ ቅድሳት ።

ካህኑም ጣቱን በደሙ እየጠለቀ ከዚሁ ደም በእግዚአብሔር ፊት በቅድስተ ቅዱሳን መጋረጃ ላይ ሰባት ጊዜ ይርጨው ። ኢሳ፡ ፵፫ ፲፱፣ ሮሜ ፫ ፳፭ ።

፯ ወይወዲ ካህን እምደሙ ለውእቱ ላሕም ላዕለ አቅርንተ ምሥዋዕ ዘዕጣን፣ ዘይወድዩ ቅድመ እግዚአብሔር ዘሀሎ ውስተ ደብተራ ዘመርጡል ።

ካህኑም ከዚህ ከበሬው ደም በደብተራ ኦሪት ውስጥ ባለው በእግዚአብሔር ፊት ዕጣን በሚያጥኑበት በዕጣኑ ምሥዋዕ ቀንዶች ያድርግ፣ (ይቀባው ይርጨው) ።

፰ ወይክዑ ኵሎ ደሞ ኀበ መንበሩ ለምሥዋዕ ዘቍርባን ዘኀበ ኆኅተ ደብተራ ዘመርጡል ።

በደብተራ ኦሪት ደጃፍ ባለው ስቡን በሚያጤሱበት መሠውያ እግር ላይ ደሙን ሁሉ ያፍስሰው ።

፱ ወኵሎ ስብሐ ለውእቱ ላሕም ዘበእንተ ኃጢአት ያሴስል ወእምስብሕ ዘይገለብብ ንዋየ ውስጡ ወኵሎ ስብሐ ዘውስተ አማዑቱ ።

ስለ ኃጢአት የተሠዋውን የዚህን በሬ ስቡን ሁሉ ይለየው፣ ሆድ ዕቃውን ከሚሸፍነው ስብ (ሞራ) ጀምሮ በአንጀቱ ላይ ያለውን ስብ ሁሉ ።

፲ ወክልኤሆን ኵልያቲሁ ወስብሐ ዘላዕሌሆን ወዘጸራዊቱ ወከብዶ እንተ ትንእስ ምስለ ኵልያቲሁ ይመትር ።

ሁለት ኵላሊቶቹን በጭቅናው በሰብራደው ያለውን ከሁለቱ ኵላሊቱ ጋር ግልገል ኵላሊቱን (ሐሞቱ) ለምለም ጉበቱን ፈቅቶ ይለየው ።

፲፩ በከመ ያወጽኡ ዘላሕመ መድኃኒት፣ ወይወድዮ ካህን ላዕለ ምሥዋዕ ዘቍርባን፣ ወማእሰኒ ለውእቱ ላሕም ወኵሎ ሥጋሁ ምስለ ርእሱ፣ ወምስለ ሰኰናሁ፣ ወከርሦ፣ ወከዕሴሁ ።

የመሥዋዕተ መድኃኒቱን ስቡን እንዲለዩ፣ ከመሥዋዕተ ኃጢአቱም ስቡን ያምጡ፣ ካህኑም ቍርባኑን በሚያቀርቡበት በመሠውያው ውስጥ ለይቶ ያኑረው፣ የላሙንም ቈርበቱንና ሥጋውንም ሁሉ ከራሱና ከሰኰናዎቹም ጋር ቀፈቱን (ፈርሱን) ከሰንበሩ ጋር ያቃጥለው ።

፲፪ ወይወስዱ አፍአ እምትዕይንት ውስተ መካን ንጹሕ ኀበ ይከዕዉ ሐመደ ወያውዕይዎ ላዕለ ዕፀው በእሳት ውስተ ምክዓወ ሐመድ ።

ይህን ሁሉ ከከተማ በአፍአ አውጥተው አመዱን ከሚያፈሱበት ከንጹሕ በታ ያፍሱት፣ ሐመቱን ከሚያፈሱበት በታ ወስደው ዕንጨት ረብርበው በእሳት ያቃጥሉት።

፲፫ ወእመሰ ለኵሉ ተዓይን ዘደቂቀ እስራኤል ተስሕቶሙ ወተረስዐት እምአዕይንቲሆሙ ቃል ለተዓይን ወገብሩ እምኵሉ ትእዛዙ ለእግዚአብሔር ዘኢይከውን ለገቢር ።

ከእስራኤል ልጆች ማኅበር ሁሉ ቢሳታቸው ግን ከዓይናቸው አንድ ቃል ቢዘነጋቸው እግዚአብሔር ካዘዘው ትእዛዝ ሁሉ ወጥተው ሊሠሩት የማይገባውን ቢሠሩ።

፲፬ ወእምዝ ነስሐ ወተዓውቀቶሙ ኃጢአቶሙ እንተ አበሱ ያመጽኡ ትዕይንቶሙ ላሕመ እምአልሕምት ንጹሐ በእንተ ኃጢአቶሙ ወያመጽእዎ ኀበ ሞኅተ ደብተራ ዘመርጡል ።

ከዚህ በኋላ ቢመለሱ (ንስሐ ቢገቡ) የሠሩዋት ኃጢአታቸው ብትታወቃቸው የእስራኤል ማኅበር ስለ ኃጢአታቸው ከላሞች ንጹሕ የሆነውን አምጥተው ወደ ደብተራ ኦሪት ያቅርቡት ። ዘፀ፡ ፳፱ ፴ ።

፲፭ ወይወድዩ ሊቃናተ ይእቲ ትዕይንት ላዕለ ርእሱ ለውእቱ ላሕም እደዊሆሙ በቅድመ እግዚአብሔር ወይጠብሕዎ ለውእቱ ላሕም ቅድመ እግዚአብሔር ።

የዚችም ጉባኤ ሽማግሌዎችም በእግዚአብሔር ፊት በዚህ በበሬው ራስ ላይ እጆቻቸውን ያኑሩ (ይጫኑ) ያንንም በሬ በእግዚአብሔር ፊት ይረዱት ። ዘፀ፡ ፳፱ ፲ ።

፲፮ ወያበውእ ካህን ዘቅቡዕ እምደሙ ለውእቱ ላሕም ውስተ ደብተራ ዘመርጡል ።

ተቀብቶ የተሾመውም ካህን የበሬውን ደም ተቀብሎ ወደ ደብተራ ኦሪት ያግባው ።

፲፯ ወይጠምዕ አፃብዒሁ ካህን ውስተ ውእቱ ደም ፤ ወይነዝኅ ስብዕ በቅድመ እግዚአብሔር ቅድመ መንጦላዕተ ቅድሳት ።

ካህኑ ጣቱን ከዚያው ደም እየጠለቀ በእግዚአብሔር ፊት በቅድስተ ቅዱሳን መጋረጃ ላይ ሰባት ጊዜ ይርጨው።

፲፰ ወይወዲ እምደሙ ካህን ላዕለ አቅርንተ ምሥዋዕ ቅድመ እግዚአብሔር ዘውስተ ደብተራ ዘመርጡል ፤ ወኵሎ ደሞ ይክዑ ኀበ መንበረ ምሥዋዕ ዘቍርባን ዘሀሎ ኀበ ሞኅተ ደብተራ ዘመርጡል ።

ካህኑም ከደሙ ዘግኖ በደብተራ ኦሪት አድሮ በለው በእግዚአብሔር ፊት ያለውን የመሠውያውን ቀንዶች ይቅባ ፤ ደሙንም ሁሉ በደብተራ ኦሪት ደጃፍ ባለው ስቡን በሚያጤሱበት በመሠውያው እግር ላይ ያፍስሰው ።

፲፱ ወኵሎ ስብሖ ያሴስል እምኔሁ ወይወድዮ ላዕለ ምሥዋዕ ።

ስቡንም ሁሉ ከርሱ ለይቶ በመሠውያው ያቃጥለው (ያጢሰው) ። ኢሳ፡ ፶፫ ፯ ፣ ማቴ፡ ፰ ፲፯ ።

፳ ወይገብሮ ለውእቱ ላሕም በከመ ይገብርዎ ለላሕም ዘኃጢአት ወያስተሠሪ ሎሙ ካህን ወይትኀደግ ሎሙ ።

ስለ ኃጢአት መሥዋዕት በታረደው በሬ ላይ እንዳደረጉት እንደዚሁ ያድርጉበት ፤ ካህኑም ኃጢአታቸውን ያስተሠርይላቸው ፤ ይሠረይላቸዋልም ። ዘኍ፡ ፲፭ ፳፭ ።

፳፩ ወይወስድዎ ለውእቱ ላሕም አፍአ እምትዕይንት ወያውዕይዎ በከመ ያውዕይዎ ለቀዳማዊ ላሕም ዘኃጢአት እስመ ዘኃጢአተ ትዕይንት ውእቱ ።

(ሊቀ ካህናቱ) የተሠዋው የፊተኛውን በሬ ሥጋውንና ቁርበቱን ከከተማው አፍአ አውጥተው እንዳቃጠሉት ይህንንም የሕዝቡን መሥዋዕተ ኃጢአት የሆነ ላህም በእሳት ያቃጥሉት ፤ የሕዝቡ ኃጢአት መሥዋዕት ነውና ።

፳፪ ወእመሰ መኰንን አበሰ ወገብረ አሐተ እምኵሉ ትእዛዘ እግዚአብሔር አምላክኮሙ ዘኢይከውን ለገቢር በኢያእምሮ ወነስሐ ወተዐውቀቶ ኃጢአቱ እንተ አበሰ ባቲ ያመጽእ ቍርባኖ ሐርጌ እምአጣሊ ንጹሐ ።

የተሾመው አገረ ገዢው ቢበድል ከፈጣሪያችሁ እግዚአብሔር ትእዛዝ ሁሉ ወጥቶ ሊሠሩዋት የማይገባ አንዲት ኃጢአት ሳይታወቀው ቢሠራ ፤ የሠራት ኃጢአቱ ተረድታው ቢመለስ (ንስሐ ቢገባ) ከፍየል ወገን ነውር የሌለበትን ንጹሕ ሙክት ለቍርባኑ ያምጣ ።

፳፫ ወይወዲ እዴሁ ላዕለ ርእሱ ለውእቱ ሐርጌ ወይጠብሕዎ ውስተ መካን ኀበ ይጠብሑ ዘይሠውዑ ቅድመ እግዚአብሔር እስመ ዘኃጢአት ውእቱ።

እጁንም በፍየሉ ሙክት ራስ ላይ ያኑር ፤ ስለ ኃጢአት የሚቀርብ ነውና ለእግዚአብሔር ከሚያጤሱበት በታ ይሠዉት ።

፳፬ ወይወዲ ካህን እምደም ዘበእንተ ኃጢአት በአፃብዒሁ ላዕለ አቅርንተ ምሥዋዕ ዘዕጣን ።

ካህኑም ከኃጢአቱ መሥዋዕት በጣቱ ወስዶ ዕጣኑን በሚያጤሱበት በአቅርንተ ምሥዋዑ በታች ያድርገው ።

፳፭ ወኵሎ ደሞ ይክዑ ላዕለ መንበረ ምሥዋዕ ዘቍርባን ።

የቀረውን ደም ሁሉ ግን ቍርባን ከሚያቀርቡበት ከእግረ ምሥዋዑ በታች ያፍስሰው ። ቍ፡ ፳ ።

፳፮ ወኵሎ ስብሖ ይወዲ ላዕለ ምሥዋዕ በከመ ስብሐ መሥዋዕት ዘመድኃኒት ፤ ወያስተሠሪ ሎቱ ካህን ወይትኀደግ ሎቱ ኃጢአቱ ።

ስቡንም ሁሉ እንደ መሥዋዕተ መድኃኒቱ ስብ በመሠውያው ላይ ያቃጥለው ፤ ካህኑም እንዲህ አድርጎ ያስተሥርይለት ፤ ኃጢአቱም ይሠረይለታል ። ዘኍ፡ ፲፭ ፳፰ ።

፳፯ ወእመሰ አሐዱ ብእሲ አበሰ እምሕዝበ ምድር በኢያእምሮ ወገብረ አሐተ እምትእዛዘ እግዚአብሔር ዘኢይከውን ለገቢር ፤ ወነስሐ ወተዐውቀቶ ኃጢአቱ እንተ ገብረ ያመጽእ ጠሊተ እምአጣሊ አንስተ ንጽሕተ በእንተ ኃጢአቱ ዘገብረ ።

በአገሩ ካሉት ሕዝብ አንድ ሰው ሳያውቅ ቢበድል ፤ ከእግዚአብሔር ትእዛዝ ወጥቶ ሊሠሩዋት የማትገባውን አንዲቱን ኃጢአት ቢሠራ ፤ ከዚህ በኋላ ቢጸጸትና የሠራት ኃጢአቱ ብትታወቀው ከፍየል ወገን ነውር የሌለበትን እንስት ፍየል ስለ ሠራት ኃጢአቱ መሥዋዕት ያምጣ።

፳፰ ወይወዲ እዴሁ ላዕለ ርእሰ ዘአምጽአ በእንተ ኃጢአቱ ወይጠብሕዋ ለይእቲ ጠሊት ዘበእንተ ኃጢአት ውስተ መካን ኀበ ይጠብሑ ዘመሥዋዕት ።

ስለ ኃጢአቱ የመጣ ሰው በመጣት እንስት ፍየል ራስ ላይ እጁን ያኑር ስለ ኃጢአት ያቀረባትንም ፍየል መሥዋዕተ ኃጢአቱን ከሚያጤሱበት በታ ይረዷት ።

፲፱ ወመሥዋዕቶሙ ወሞጻሕቶሙ ለአልሕምትኒ ወለአበግዕኒ ወለመሐስአ አባግዕኒ በበኍላቍሆሙ በከመ ሕጎሙ ።

ፍልቅ አድርገው የሚጠጡትና መሥዋዕታቸውም ለላሞችም ለበጎች ጠቦቶችም በየቍጥራቸው እንደ ሕጋቸው ነው ። ዘኍ፡ ፳፱ ፳፡ ፲፰ ፲፱ ።

፳ ወሐርጌ አሐደ እምአጣሊ በእንተ ኃጢአት ዘእንበለ መሥዋዕት ዘዘልፍ ወመሥዋዕቶሙ ወሞጻሕቶሙ ።

ከዘወትሩ መሥዋዕት በቀር ስለ ኃጢአት ከፍየሎች አንድ ሙክት ሠዉ ፡ መሥዋዕታቸውም ፍልቅ አድርገው የሚጠጡት ወይኑም እንደዚሁ ነው ።

፳፩ <u>ወበሣልስት ዕለት</u> ዓሠርተ ወአሐደ አሥዋረ ወክልኤተ አባግዐ ፡ ወመሐስአ አባግዕ ዓሠርተ ወአርባዕተ ንጹሓነ ዘዘዓመት ።

<u>በሦስተኛይቱም ቀን</u> ሁለት በጎችንና ዓሥር ገቾችን ንጹሐን የሆኑ አንድ አንድ ዓመት የሆናቸው ዓሥራ አራት የበጎች ጠቦቶችን ሠዉ ።

፳፪ ወመሥዋዕቶሙ ወሞጻሕቶሙ ለአልሕምትኒ ወለአበግዕኒ ወለመሐስአ አባግዕኒ በበኍላቍሆሙ በከመ ሕጎሙ ።

መሥዋዕታቸውና ፍልቅ አድርገው የሚጠጡት ወይኑም ለላሞችም ለበጎችም ለበጎች ጠቦቶችም እንደ ሥርዓታቸው በየቍጥራቸው ነው ።

፳፫ ወሐርጌ አሐደ እምአጣሊ በእንተ ኃጢአት ዘእንበለ መሥዋዕት ዘዘልፍ ወመሥዕዋቶሙ ወሞጻሕቶሙ ።

ከዘወትሩ መሥዋዕትም በቀር ስለ ኃጢአት ከፍየሎች አንድ ሙክት ሠዉ ፤ ፍልቅ አድርገው የሚጠጡትና መሥዋዕታቸውም እንደዚሁ ነው ።

፳፬ <u>ወበራብዕት ዕለት</u> ዐሠርተ አሥዋረ ወክልኤተ አባግዐ ወዓሠርተ ወአርባዕተ መሐስአ አባግዕ ንጹሓነ ዘዘዓመት ።

<u>በአራተኛይቱም ቀን</u> ሁለት በጎችንና አሥር ገቾችን ያንዳንድ ዓመት ንጹሐን የሆኑ ዓሥራ አራት የበጎች ጠቦቶችን ሠዉ ።

፳፭ ወመሥዋዕቶሙ ወሞጻሕቶሙ ለአልሕምትኒ ወለአበግዕኒ ወለመሐስአ አባግዕኒ በበኍላቍሆሙ በከመ ሕጎሙ ።

ፍልቅ አድርገው የሚጠጡትና መሥዋዕታቸውም ለላሞችም ለበጎችም ለበጎች ጠቦቶችም በየቍጥራቸው እንደ ሥርዓታቸው ነው ።

፳፮ ወሐርጌ አሐዱ እምአጣሊ በእንተ ኃጢአት ዘእንበለ መሥዋዕት ዘዘልፍ ፡ ወመሥዋዕቶሙ ወሞጻሕቶሙ ።

ከዘወትሩ መሥዋዕት በቀር ስለ ኃጢአት ከፍየሎች አንድ ሙክት ሠዉ ፤ ፍልቅ አድርገው የሚጠጡትና መሥዋዕታቸውም እንደዚሁ ነው ።

፳፯ <u>ወበሐምስ ዕለት</u> ተስዓተ አሥዋረ ወክልኤተ አባግዐ ወዓሠርተ ወአርባዕተ መሐስአ አባግዕ ንጹሓነ ዘዘዓመት ።

<u>በአምስተኛይቱም ቀን</u> ሁለት በጎችንና ዘጠኝ ገቾችን ንጹሐን የሆኑ ዓመት ዓመት የሆናቸው ዓሥራ አራት የበጎች ጠቦቶችን ሠዉ ።

፳፰ ወመሥዋዕቶሙ ወሞጻሕቶሙ ለአልሕምትኒ ወለአበግዕኒ ወለመሐስአ አባግዕኒ በበኍላቍሆሙ በከመ ሕጎሙ ።

ፍልቅ አድርገው የሚጠጡትና መሥዋዕታቸውም ለላሞችም ለበጎችም ፡ ለበግ ጠቦቶችም እንደ ሥርዓታቸው በየቍጥራቸው ነው ።

፳፱ ወሐርጌ አሐደ እምአጣሊ በእንተ ኃጢአት ዘእንበለ መሥዋዕት ዘዘልፍ ፡ ወመሥዋዕቶሙ ወሞጻሕቶሙ ።

ከዘወትሩ መሥዋዕትም በቀር ስለ ኃጢአት ከፍየሎች አንድ ሙክት ሠዉ ፤ ፍልቅ አድርገው የሚጠጡት ወይኑና መሥዋዕታቸውም እንደዚሁ ነው ።

፴ <u>ወበሳድስት ዕለት</u> ሰመንተ አሥዋረ ወክልኤተ አባግዐ ወዐሠርተ ወአርባዕተ መሐስአ አባግዕ ንጹሓነ ዘዘዓመት ።

<u>በስድስተኛይቱም ቀን</u> ሁለት በጎችንና ስምንት ገቾችን ንጹሐን የሆኑ የአንድ አንድ ዓመት ዓሥራ አራት የበጎች ጠቦቶችን ሠዉ ።

፴፩ ወመሥዋዕቶሙ ወሞጻሕቶሙ ለአልሕምትኒ ወለአበግዕኒ ወለመሐስአ አባግዕኒ በበኍላቍሆሙ በከመ ሕጎሙ ።

ፍልቅ አድርገው የሚጠጡትና መሥዋዕታቸውም ለላሞችም ለበጎችም ለበግ ጠቦቶችም እንደ ሥርዓታቸው በየቍጥራቸው እንደዚሁ ነው ።

፴፪ ወሐርጌ አሐደ እምአጣሊ በእንተ ኃጢአት ዘእንበለ መሥዋዕት ዘዘልፍ ወመሥዋዕቶሙ ወሞጻሕቶሙ ።

ከዘወትሩ መሥዋዕትም በቀር ስለ ኃጢአት ከፍየሎች አንድ ሙክት ሠዉ ፤ ፍልቅ አድርገው አፍሰው የሚጠጡትና መሥዋዕታቸውም እንደዚሁ ነው ።

፴፫ <u>ወበሳብዕት ዕለት</u> ሰብዓተ አሥዋረ ወክልኤተ አባግዐ ወዓሠርተ ወአርባዕተ መሐስአ አባግዕ ንጹሓነ ዘዘዓመት ።

<u>በሰባተኛይቱም ቀን</u> ሁለት በጎችንና ሰባት ገቾችን ንጹሐን የሆኑ ያንዳንድ ዓመት ዓሥራ አራት የበጎች ጠቦቶችን ሠዉ ።

፴፬ ወመሥዋዕቶሙ ወሞጻሕቶሙ ለአልሕምትኒ ወለአበግዕኒ ወለመሐስአ አባግዕኒ በበኍላቍሆሙ በከመ ሕጎሙ ።

ፍልቅ አድርገው የሚጠጡት ወይኑና መሥዋዕታቸውም ለላሞችም ለበጎችም ለበግ ጠቦቶችም እንደ ሥርዓታቸው በየቍጥራቸው እንደዚሁ ነው ።

፴፭ ወሐርጌ አሐደ እምአጣሊ በእንተ ኃጢአት ዘእንበለ መሥዋዕት ዘዘልፍ ወመሥዋዕቶሙ ወሞጻሕቶሙ ።

ከዘወትሩም መሥዋዕት በቀር ስለ ኃጢአት ከፍየሎች አንድ ሙክት ሠዉ፣ ፍልቅ አድርገው የሚጠጡትና መሥዋዕታቸውም እንደዚሁ ነው ።

፴፮ ወበሳምንት ዕለት ዕለተ ተሐውሶ ይእቲ ለክሙ ፤ ኵሎ ግብረ ማሕረስ ኢትግበሩ ባቲ ።

በስምንተኛይቱም ቀን ለናንተ በዓለ ተሐውሶ ናት፣ አትረሱበት አትቈፍሩበት ።

፴፯ ወአብኡ መሥዋዕተ ወቍርባነ ለሠናይ መዓዛ ለእግዚአብሔር ስሒመ አሐደ ወበግዐ አሐደ ለመሥዋዕት ፤ ወሰብዐተ መሐስአ አባግዕ ንጹሐነ ዘዘዓመት ።

እግዚአብሔር ወዶ ሊቀበለው የምትሠዉትንና የምታቀርቡትን አንድ በግንና አንድ ላምን አንዳንድ ዓመት የሆናቸው ንጹሐን የሆኑ ሰባት የበጎች ጠቦቶችን ሠዉ ።

፴፰ ወመሥዋዕቶሙ ወሞጻሕቶሙ ለላሕምኒ ወለበግዕኒ ወለመሐስአ አባግዕኒ በበኍላቌሆሙ በከመ ሕጎሙ ።

ፍልቅ አድርገው የሚጠጡትና መሥዋዕታቸውም ለላሞችም ለበጎችም ለበግ ጠቦቶችም እንደየ ሥርዓታቸው በየቍጥራቸው ነው ።

፴፱ ወሐርጌ አሐደ እምአጣሊ በእንተ ኃጢአት ዘእንበለ መሥዋዕት ዘዘልፍ ወመሥዋዕቶሙ ወሞጻሕቶሙ ።

ከዘወትሩ መሥዋዕት በቀር ስለ ኃጢአት ከፍየሎች አንድ ሙክት ሠዉ፣ ፍልቅ አድርገው የሚጠጡት ወይንና መሥዋዕታቸውም እንደዚሁ ነው ።

፵ ወከመዝ ግበሩ ዘንተ በበዓላቲክሙ ለእግዚአብሔር ።

በፈቃዳችሁ ከምታገቡት ሌላ በበዓላቶቻችሁ ለእግዚአብሔር ብላችሁ እንደዚህ አድርጉ ።

፵፩ ዘእንበለ ዘበፈቃድክሙ ፤ ወቍርባንክሙኒ ወመሥዋዕቲክሙኒ ወሞጻሕቲክሙኒ ወዘመድኃኒትክሙኒ ።

ቍርባናችሁም መሥዋዕታችሁም ፍልቅ አድርጋችሁ የምትጠጡት ወይናችሁና ድኅነትን የሚያሰጣችሁ መሥዋዕትም እንደዚሁ ነው አላቸው ። ዘሌ፡ ፳፫ ፩ ።

፵፪ ወነገሮሙ ሙሴ ለደቂቀ እስራኤል ኵሎ ዘከመ አዘዘ እግዚአብሔር ።

ሙሴም እግዚአብሔር እንዳዘዘው ለእስራኤል ልጆች ሁሉን ነገራቸው ። ፩ ዜና መ፡ ፳፫ ፴፩ ፣ ዘዳ፡ ፴፩ ፳፯ ።

## ምዕራፍ ፴ ።

፩ ወነገሮሙ ሙሴ ለመላእክተ ሕዝብ ዘደቂቀ እስራኤል ወይቤሎሙ ፤ ዝንቱ ውእቱ ቃል ዘአዘዘ እግዚአብሔር ።

ሙሴ እግዚአብሔር ያዘዛችሁ ይህ ነው ብሎ ለእስራኤል ልጆች ወገኖች አለቆች ነገራቸው ።

፪ ብእሲ ብእሲ ለእመ በፅዐ ብፅዐተ ለእግዚአብሔር ወለእመኒ መሐለ መሐላ ፤ አው ፈለጠ ፍሉጠ በእንተ ነፍሱ ፤ ኢያገምን ኵሎ ቃሎ ዘወፅአ እምአፉሁ ይግበር ።

አንዱም አንዱም ሰው ለእግዚአብሔር ስለት ቢሳል እሰጣለሁ ብሎም መሐላን ቢምል ወይም ስለ ሰውነቱ ይህን እሰጣለሁ ብሎ የለየው መለየት ቢኖር ከአንደበቱ የወጣውን ቃል ሁሉ አያስቀር (ያድርግ) ።

፫ ወለእመኒ ብእሲት በፅዐት ብፅዐተ ለእግዚአብሔር አው ፈለጠት ፍሉጠ በቤተ አቡሃ በንእስ ወሰምዐ አቡሃ ጸሎታ ወኵሎ ብፅዐታ ዘበፅዐት በእንተ ነፍሳ ወተጸመማ አቡሃ ይቀውም ላዕሌሃ ኵሉ ጸሎታ ወኵሉ ብፅዓቲሃ ዘበፅዓት በእንተ ነፍሳ ።

ሴትም ለእግዚአብሔር ስለትን ብትሳል ፤ ወይም በባቷ ቤት በሕፃንነቷ ይህን እሰጣለሁ ብላ ለይታ ብትሳል ፣ አባቷም ስለቷን ሰምቶ ቸል ቢላት ፣ ስለቷ ሁሉ በቧ ይጸናል ፤ ስለ ሰውነቷ የተሳለችው ስለቷ ሁሉ በቧ ጸንቶ ይኖራል ። ዘኍ፡ ፴ ፳፯ ፣ መክ፡ ፶፮ ፲፪ ።

፬ ወለእመሰ ገብረ ላቲ አቡሃ ወፈጸመ በዕለተ ሰምዐ ኵሎ ጸሎታ ወብፅዐቲሃ ዘበፅዓት በእንተ ነፍሳ ኢይነብር ላዕሌሃ ፤ ወያነጽሓ እግዚአብሔር በዕለተ ገብረ ላቲ አቡሃ ።

አባቷ ቢያደርግላት ግን ስለ ሰውነቷ የተሳለችው ስለቷን ሁሉ በሰማበት ቀን ቢፈጽምላት በቧ ጸንቶ አይኖርም አባቷ ባደረገላትም ቀን እግዚአብሔር ያነጻታል ።

፭ ወለእመሰ አውሰበት ብእሴ ወሀለወ ላዕሌሃ ጸሎታ በከመ ነበበት በከናፍሪሃ ኵሉ ዘበፅዐት በእንተ ነፍሳ ።

ባል ብታገባ ግን ስለ ሰውነቷ የተሳለችው ስለቷን ሁሉ በአንደበቷ እንደ ተናገረች ስለቷ በላይዋ ላይ ነው።

፮ ወሰምዐ ምታ ወተጸመማ በዕለተ ሰምዐ ከማሁ ይቀውም ላዕሌሃ ኵሉ ጸሎታ ወብፅዓቲሃ ዘበፅዐት በእንተ ነፍሳ ።

ባሏም ሰምቶ በሰማበት ቀን ቸል ቢላት ስለ ሰውነቷ የተሳለችው ስለቷ ሁሉ እንደዚሁ በርሷ ጸንቶ ይኖራል ።

፯ ወለእመሰ ገብረ ላቲ ምታ ወፈጸመ በዕለተ ሰምዐ ኵሎ ጸሎታ ወብፅዓቲሃ ዘበፅዐት በእንተ ነፍሳ ኢይነብር ላዕሌሃ እስመ ገብረ ላቲ ምታ ወያነጽሓ እግዚአብሔር ።

ባሏ ቢያደርግላት ግን ስለ ሰውነቷ የተሳለችው ስለቷን ሁሉ በሰማበት ቀን ቢፈጽምላት ባሏ ፈጽሞላታልና በቧ ጸንቶ አይኖርም ፣ እግዚአብሔር ያነጻታል ።

፰ ወጸሎታሂ ለመበለት ወለእንተ እውጽአ ምታ ኵሉ ዘበፅዐት በእንተ ነፍሳ ይሄሉ ላዕሌሃ ።

የጋለሞታዋም ስለት፣ ባሏ የፈታትም ፣ ስለ ሰውነቷ የተሳለችው ስለት ሁሉ በርሷ ጸንቶ ይኖራል ።

፲፪ ወለእመሰ እንዘ ሀለወት በቤተ ምታ ጸለየት ወበፅዐት በአንተ ነፍሳ ወሰምዐ ምታ ወተጸመማ ወኢገብረ ላቲ ኵሉ ጸሎታ ወኵሉ ብፅዓቲሃ ዘበፅዓት በአንተ ነፍሳ ይቀውም ዲቤሃ ።

በባሏም ቤት ሳለች ስለ ሰውነቷ ብትሳል ፥ ባሏም ሰምቶ ቸል ቢላት ስለ ሰውነቷ የተሳለችውም ስለት ባያደርግላት በርሷ ጸንቶ ይኖራል ።

፲፫ ወለእመሰ ገብረ ላቲ ምታ ወፈጸመ በዕለተ ሰምዐ ኵሎ ዘወፅአ እምከናፍሪሃ ዘከመ ጸለየት ወዘከመ በፅዐት በአንተ ነፍሳ ኢይነብር ላዕሌሃ እስመ ገብረ ላቲ ምታ ወያነጽሓ እግዚአብሔር ።

ባሏ ቢያደርግላት ግን ስለ ሰውነቷ እንደ ተሳለች ከአንደበቷ የወጣውን ስእሏን ሁሉ በሰማበት ቀን ቢፈጽምላት ባሏ አድርጎላታልና በርሷ ጸንቶ አይኖርም ፥ እግዚአብሔርም ያነጻታል ።

፲፬ ወኵሎ ብፅዓተ ወኵሎ ማእሰረ መሐላ ዘይከውን እኩየ ላዕለ ነፍሳ ያቀውም ምታ ወይገብር ላቲ ።

በሰውነቷ ክፉ የሚሆን በፍዳ የሚያስይዝ መሐላውንና ስለቱን ሁሉ ባሏ ያጸናበታል ፅዳም ያደርግበታል ።

፲፭ ወለእመሰ ተጸመማ ዕለተ እምዕለት ኵሎ ጸሎታ ወብፅዓቲሃ ይቀውም ዲቤሃ እስመ ተጸመማ በዕለተ ሰምዐ ።

ከቀን ቀን እያለ ቸል ቢላት ግን በሰማበት ቀን ቸል ብሏታልና ስለቷ ሁሉ በርሷ ጸንቶ ይኖራል ።

፲፮ ወለእመሰ ገብረ ላቲ እምድኅረ ዕለት እንተ በቲ ሰምዐ ኢይከውኖ ኃጢአተ ።

ከሰማበት ቀን በኋላ ቢያደርግላት ግን ኃጢአት አይሆንበትም ። ዘሌዋ፡ ፳ ፩ ።

፲፯ ዝንቱ ውእቱ ኵነኔ ኵሉ ዘአዘዘ እግዚአብሔር ለሙሴ ማእከለ ብእሲ ወብእሲቱ ወማእከለ አብ ወወለቱ በንእሳ እንዘ ሀለወት ቤተ አቡሃ ።

በሚስቱና በባሏ መካከል በአባቷ ቤት ሳለች በሕፃንነቷ የሚደረግ በልጅና በአባት መካከል የሚደረግ እግዚአብሔር ለሙሴ ያዘዘው ሥርዓት ይህ ነው ።

## ምዕራፍ ፴፩ ።

፩ ወነበበ እግዚአብሔር ለሙሴ ወይቤሎ ፥ ተበቀል በቀሎሙ ለደቂቀ እስራኤል እመድናውያን ወድኅረ ትትዌሰክ ኀበ ሕዝብከ ።

እግዚአብሔር ሙሴን ተናገረው እንዲህም አለው ፥ ከምድያም ሰዎች የእስራኤልን ልጆች በቀል መልስ ከዚያም በኋላ በሞት ወደ ወገኖችህ ትጨመራለህ ።

፪ ወነገሮሙ ሙሴ ለሕዝብ ወይቤሎሙ አስተጋብኡ እምኔክሙ አደወ ወተቃተሉ ቅድመ እግዚአብሔር ምስለ ምድያም ከመ ያግብኡ በቀለ እምኀበ እግዚአብሔር ለምድያም ።

ሙሴም ለሕዝቡ ከናንተ ሰዎችን ሁሉ ሰብስቡቸው ስለ እግዚአብሔር በቀል የምድያምን ሰዎች ይበቀሉ ዘንድ በእግዚአብሔር ፊት ከምድያም ሰዎች ጋራ ተዋጉ ብሎ ነገራቸው ። ዘኍ፡ ፳፭ ፲፯ ፣ ፩ ፳፱ ።

፫ ወዐሠርተ ምእተ እምነገድ ፥ ወዓሠርተ ምእተ እምነገድ እምኵሉ ነገደ እስራኤል ፈንዉ ዘይትቃተል ።

ከእስራኤል ነገድ ሁሉ የሚዋጋ ከንዱ ነገድ ሺሕ ከንዱም ነገድ ሺሕ ሰው ላኩ ። ዘኍ፡ ፴፱ ፳፯ ።

፬ ወኆለቁ እምአእላፍ ዘእስራኤል እምነገድ ነገድ ዐሠርተ ምእተ ፥ ወኮኑ አልፈ ወዕሥራ ምእተ እለ ተረሰዩ ለቀትል ።

ከእስራኤል ሠራዊት ከየወገን ከየወገኑ ሺሕ ሺሕ ሰው ቍጠሩ ለሰልፍ የተዘጋጁት አልፍ ከሁለት ሺሕ ኾኑ። ኢያ፡ ፬ ፲፫ ።

፭ ወፈነዎሙ ሙሴ በበዐሠርቱ ምእት ዘዘነገድ ነገድ ፥ ምስለ ኀይሎሙ ።

ሙሴም ከየነገዱ ነገድ ከሠራዊቶቻቸው ጋር ሺሕ ሺሕ እያደረገ ላካቸው ።

፮ ወፊንሐስ ወልደ አልአዛር ወልደ አሮን ካህን ወንዋየ ቅድሳት ወመጣቅዕት ዘተአምር ምስሌሆሙ ።

የካህን የአሮን ልጅና የአልአዛር ልጅ ፊንሐስም ነበሩ ፥ ምልክት የሚደረግባቸው ነጋሪቶችና ንዋየ ቅድሳቱም ከነሱ ጋር ነበሩ ። ዘኍ፡ ፲፯ ፱ ፣ ዘሌ፡ ፳፫ ፳፬ ።

፯ ወተቃተልዎሙ ለምድያም በከመ አዘዘ እግዚአብሔር ለሙሴ ወቀተሉ ኵሎ ተባዕቶሙ ።

እግዚአብሔር ሙሴን እንዳዘዘው የምድያምን ሰዎች ወንዋቸው ወንድ ወንዱን ሁሉም አጠፉ ። ዘዳ፡ ፳ ፲፫ ።

፰ ወለነገሥተ ምድያምሂ ቀተልዎሙ ኅቡረ በውእቱ ቀትሎሙ ለኤዎን ወለሮቆምሂ ወለሱርሂ ወለሑርሂ ወለሩበቅሂ ኃምስቱ ነገሥተ ምድያም ወለበለዓምሂ ወልደ ቤዖር ቀተልዎ በሐጺን በውእቱ ቀትሎሙ ።

የምድያምንም ነገሥታት ሮቆምንና ኤዎንን ሱርንና ሩባቅን አምስቱን የምድያም ነገሥታት በዚያው ሰልፍ አንድነት ገደሉዋቸው ፥ የቢዖር ልጅ በለዓምንም በዚያ ሰልፋቸው በጦር ገደሉት ።

፱ ወፄወዉ አንስትያሆሙ ለምድያም ወሕፃናቲሆሙኒ ወእንስሳሆሙኒ ወኵሎ ጥሪቶሙ ወኀይሎሙ በርበሩ ።

የምድያምን ሴቶች ልጆቻቸውንም ከብቶቻቸውንም ገንዘባቸውንም ሁሉ ማረኩ ፥ ሠራዊቶቻቸውንም ሁሉ ዘረፉ ። ዘፍ፡ ፴፬ ፳፱ ።

፲ ወኵሎ አህጉሪሆሙ ዘይነብሩ ውስቴቶን ፥ ወአዕፃዳቲሆሙኒ አውዐዩ በእሳት ።

የሚኖሩባቸው አገሮቻቸውን ሁሉ ፥ ቦታዎቻቸውንም ሁሉ በእሳት አቃጠሉ ።

፲፩ ወነሥኡ ኵሎ ፄዋሆሙ ወምህርካሆሙ እምሰብእ እስከ እንስሳ ።

የከብት ምርኮና የሰውን ምርኮ ሁሉ ከሰው ጀምሮ እስከ ከብት ድረስ ወሰዱ ። ዘዳ፡ ፳ ፲፬ ።

| | | |
|---|---|---|
| ወወሰዱ ኀበ ሙሴ ወኀበ አልአዛር ካህን ወኀበ ኵሉ ደቂቀ እስራኤል ፄዋ ወምህርካ ወዘበርበሩ ውስተ ትዕይንት በአራብት ዘሞዓብ እንተ ኀበ ዮርዳኖስ ዘመንገለ ኢያሪኮ ። | ፲፪ | ወደ ካህኑ ወደ አልአዛርና ወደ ሙሴ ወደ እስራኤልም ልጆች ሁሉ ዘንድ የማረኩትን ምርኮ ወሰዱ ፣ በዮርዳኖስ ማዶ የኢያሪኮ አንጻር በምትሆን በሞዓብ በአራበት ከተማ የዘረፉትንም ወሰዱ ። ዘኍ፡ ፳፪ ፩ ። |
| ወወፅኡ ሙሴ ወአልአዛር ካህን ወኵሉ መላእክተ ተዓይን ወተቀበልዎሙ አፍአ እምትዕይንት ። | ፲፫ | ካህኑ አልአዛርና ሙሴ የሠራዊቱም አለቆች ሁሉ ወጥተው ከከተማው ውጪ ተቀበሉዋቸው ። |
| ወተምዐ ሙሴ መበተ ላዕለ ሠራዊት ወላዕለ መሳፍንቲሆሙ ወላዕለ መላእክቲሆሙ እለ አተዉ እምጸብእ እምኀበ ይትቃተሉ ። | ፲፬ | ሙሴም በሹማምንቱና በሠራዊቱ ከሚዋጉበት ሰልፍ በተመለሱ በአለቆችም ላይ ቍጣን ተቈጣ ። |
| ወይቤሎሙ ሙሴ ለምንት አሕየውክሙ ኵሎ አንስት እስመ እማንቱ ውእቶን እለ ይከውናሆሙ ዕቅፍተ ለደቂቀ እስራኤል ። | ፲፭ | ሙሴም ለእስራኤል ልጆች መሰናክል የሚሆኑዋቸው እነዚህ ናቸውና ሴቶቹን ሁሉ ለምን አዳናችሁ ፤ ። ዘኍ፡ ፴፩ ፲፱ ፣ ዘሌዋ፡ ፬ ፲፪ ። |
| በከመ ይቤ በለዓም እለ ያስሕታሆሙ ወያኅድጋሆሙ ቃለ እግዚአብሔር በበይነ ፌጎር ወመጽአ መቅሠፍተ እግዚአብሔር ላዕለ ትዕይንት ። | ፲፮ | በለዓም በጣኦቱ ምክንያት የሚያስቷቸውና የእግዚአብሔርን ቃል የሚያስተውዋቸው እሊህ ናቸው ብሎ እንደ ተናገረ በነሱም ምክንያት ከእግዚአብሔር ታዝዞ መቅሠፍት መጥቷልና ለምን አዳናችሁ ፤ ብሎ ተቈጣ ። |
| ወይእዜኒ ቅትሉ ኵሎ ተባዕተ በኀበ ሀሰዉ ወኵሎ ብእሲተ እንተ አእመረት ብእሴ ቅትሉ ። | ፲፯ | አሁንም ወንድ ወንዱን ሁሉ በየአሉበት በታ ግደሉ ለወንድ የደረሰችንም ሴት ግደሉ ። መሳ፡ ፳፩ ፲፪ ። |
| ወኵሎ አዋልደ እለ ኢያእመራ ብእሴ አሕይዉ ወአንትሙኒ ትዓየኑ አፍአ እምትዕይንት ሰቡዐ መዋዕለ ። | ፲፰ | ከወንድ ያልደረሱ ሴቶችን ግን አድኑ ፣ (አትግደሉ) እናንተም ሰባት ቀን ከከተማው ውጭ ሰፈሩ ። |
| ኵሉ ዘቀተለ ወዘገሠሠ ምዉተ ያንጽሕ ርእሶ አመ ሣልስት ዕለት ወአመ ሳብዕት አንትሙ ወፄዋክሙ ። | ፲፱ | ነፍስ የገደለ ፣ ሬሳን የዳሰሰ ሰው ሁሉ በሦስተኛው ቀን ራሱን ንጹሕ ያድርግ ፣ በሰባተኛይቱ ቀን ደግሞ እናንተም ምርኮቻችሁም ራሳችሁን ንጹሕ አድርጉ አላቸው ። |
| ወኵሎ ልብሰ ወኵሎ ንዋየ ማእስ ወኵሎ ንዋየ ዘማእሰ ጠሊ ወኵሎ ንዋየ ዕፅ አንጽሑ ። | ፳ | ልብስንም ሁሉ ከቈርበቱም ወገን ሁሉ (ዳውላን) ከፍየል ወገን የሚሆን ሌጦውን ሁሉ ሰደቃውን ገበታውን ሁሉ ንጹሕ አድርጉ ። ዘሌዋ፡ ፲፫ ፵፱ ፣ ፲፭ ፲፬ ። |
| ወይቤሎሙ አልአዛር ለአደወ ኀይል እለ አተዉ እምጸብእ እምኀበ ይትቃተሉ ዝንቱ ውእቱ ኵነኔሁ ለሕግ ዘአዘዘ እግዚአብሔር ለሙሴ ። | ፳፩ | አልአዛርም ከሚዋጉበት ሰልፍ የተመለሱ አርበኞችን እግዚአብሔር ሙሴን ያዘዘው የሕጉ ቅጣት ይህ ነው አላቸው ። |
| ኵሉ ወርቅ ወብሩር ወብርት ወሐፂን ወዓረር ወናእክ ወኵሉ ንዋይ ዘይትገበር በእሳት ይነጽሕ ወያንጽሕዎ ። | ፳፪ | ወርቁ ፣ ብሩና ብረቱ ፣ ናሱና ቆልቆሉ ሁሉ ፣ የሚሠራበት ዕቃ ሁሉ በእሳት ይጸራል ፣ (ይነጻል) ። |
| በማየ አንጽሖ ወለኵሉ ዘኢይበውእ ውስተ እሳት ለይጥምዕዎ ውስተ ማይ ። | ፳፫ | በሚያነጹበትም ጊዜ በውኃ ያንጹት ወደ እሳት የማይገባውን ዕቃ ሁሉ ግን በውኃ ይንከሩት ። ዘኍ፡ ፲፱ ፱ ። |
| ወሕፅቡ አልባሲክሙ በሳብዕት ዕለት ወትነጽሑ ፣ ወእምድኅረ ዝንቱ ትበውኡ ውስተ ትዕይንት ። | ፳፬ | በሰባተኛይቱም ዕለት ልብሳችሁን እጠቡ ከኃጢአትም ትነጻላችሁ ፣ ከዚያም በኋላ ወደ ከተማው ግቡ አላቸው ። |
| ወነበበ እግዚአብሔር ለሙሴ ወይቤሎ ፡ ንሣእ መሠንዮ ለፄዋ ወለምህርካ እምሰብእ እስከ እንስሳ አንተ ወአልአዛር ወመላእክተ አበዊሆሙ ለተዓይን ። | ፳፭ | እግዚአብሔር ሙሴን እንዲህ ሲል ተናገረው ፤ ከከብቱ ምርኮና ከሰው ምርኮ ያማረ የማረውን ፤ ከሰው ጀምሮ እስከ ከብቱ ድረስ አንተና አልአዛር የሠራዊቱን አባቶች አለቆችን ይዘህ ። ፩ ሳሙ፡ ፴ ፳፬ ። |
| ወትከፍሉ ምህርካ ማእከሎሙ ለእለ ፀብኡ ወለእለ ሖሩ ይትቃተሉ ወማእከለ ኵሉ ተዓይን ። | ፳፮ | ሊዋጉ በሄዱት መካከልና በሰልፍ በዋሉት በሠራዊቱም መካከል ምርኮውን ክፈሉ ። ኢያሱ ፳፪ ፰ ። |
| ወታወጽኡ ጸባሕቶ ለእግዚአብሔር እምኀቤሆሙ ለእለ ፀብኡ ወለእለ ሖሩ ይትቃተሉ አሐተ ነፍሰ እምሐምስቱ ምእት ሰብእ ወእምእንስሳ ወእምአልሕምት ወእምአባግዕ ወእምአእዱግ ። | ፳፯ | ይዋጉ ዘንድ ወደ ሰልፍ ከሄዱት ፤ ከአምስት መቶ ሰዎች ዓሥራቱን ለእግዚአብሔር አንድ ሰው አውጡ ፣ ከላሙና ከፈረሱ ከበቅሎው ከአህዮች ከበጎችም ከአምስት መቶ አንድ አውጡ አላቸው ። ዘኍ፡ ፲፰ ፳፮ ። |
| ወትነሥኡ እመንፈቆሙ ወትሁቡ ለአልአዛር ካህን ቀዳምያቲሁ ለእግዚአብሔር ። | ፳፰ | ከእኩሌታቸው ተቀብለህ ለካህኑ ለአልአዛር የእግዚአብሔር ዓሥራቱን ስጠው ። ፩ ሳሙ፡ ፴ ፳፬ ። |
| ወእመንፈቆሙ ለደቂቀ እስራኤል ትነሥእ አሐደ እምኀምሳ እምሰብእ ወእምአልሕምት ወእምአባግዕ ወእምአ | ፳፱ | ከእስራኤል ልጆች እኩሌታም ከበጎችና ከላሞች ከፈረሶችና ከበቅሎች ከአህዮችም ከአምሳ አንድ ተቀብለህ |

እዱግ ወእምእንስሳ ወሀቦሙ ለሌዋውያን እለ የዐቅቡ ሕገ ደብተራሁ ለእግዚአብሔር ።

፴ ወገብሩ ሙሴ ወአልአዛር ካህን በከመ አዘዘ እግዚአብሔር ለሙሴ ።

፴፩ ወኮነ ኍልቈ አባግዕ ዘማህረኩ እደው እለ ፀብኡ ስሳ ወሰብዓቱ እልፍ ወሐምሳ ምእት ።

፴፪ ወአልሕምት ሰብዓቱ እልፍ ወዕሥራ ምእት ።

፴፫ ወአእዱግ ሰብዓቱ እልፍ ወዓሠርቱ ምእት ።

፴፬ ወሰብእ ዘመንፈሰ አንስት እለ ኢያእመራ ብእሲ፣ ሠለስቱ እልፍ ወዕሥራ ምእት ።

፴፭ ወኮነ መንፈቀ ክፍሎሙ ለእለ ሖሩ ፀብአ እምኍልቈ አባግዕ ሠላሳ ወሠለስቱ እልፍ፣ ሰብዓ ምእት፣ ወሐምስቱ ምእት ።

፴፮ ወኮነ ጸባሕቱ ለእግዚአብሔር እምአባግዕ ሰብዓቱ ምእት ሰብዓ ወሐምስቱ ።

፴፯ ወአልሕምት፣ ሠለስቱ እልፍ ወስሳ ምእት ።

፴፰ ወኮነ ጸባሕቱ ለእግዚአብሔር፣ ሰብዓ ወክልኤቱ ።

፴፱ ወአእዱግ ሠለስቱ እልፍ፣ ወሐምስቱ ምእት ።

፵ ወኮነ ጸባሕቱ ለእግዚአብሔር፣ ስሳ ወአሐዱ ።

፵፩ ወሰብእ ዘመንፈስ፣ እልፍ ወስሳ ምእት ።

፵፪ ወኮነ ጸባሕቱ ለእግዚአብሔር፣ ሠላሳ ወክልኤቱ ።

፵፫ ወወሀበ ሙሴ ጸባሕተ ዘፈለጡ ለእግዚአብሔር ለአልአዛር ካህን፣ በከመ አዘዘ እግዚአብሔር ለሙሴ ።

፵፬ ወእመንፈቆሙ ለደቂቀ እስራኤል ዘአውጽአ ሙሴ እምእደው እለ ሖሩ ፀብአ ።

፵፭ ወኮነ መንፈቁ ለዝ እምትዕይንት፣ እምአባግዕ፣ ሠላሳ ወሠለስቱ እልፍ፣ ወሰብዓ ምእት፣ ወሐምስቱ ምእት ።

፵፮ ወአልሕምት፣ ሠለስቱ እልፍ፣ ወስሳ ምእት ።

፵፯ ወአእዱግ ሠለስቱ እልፍ፣ ወሐምስቱ ምእት ።

፵፰ ወሰብእ ዘመንፈስ እልፍ ወስሳ ምእት ።

፵፱ ወነሥአ ሙሴ መንፈቆሙ ለደቂቀ እስራኤል አሐደ እምሐምሳ፤ እምሰብእ ወእምእንስሳ፣ ወወሀቦሙ ለሌዋውያን እለ የዐቅቡ ሕገ ደብተራሁ ለእግዚአብሔር በከመ አዘዘ እግዚአብሔር ለሙሴ ።

፶ ወመጽኡ ኀበ ሙሴ ኵሎሙ መላእክተ ዐሠርቱ ምእት ሠራዊት ወመላእክተ ምእት፣ ወይቤልዎ ለሙሴ ።

፶፩ አግብርቲከ ነሥኡ ሠርጐሆሙ ለእደው እለ ቀተሉ ምስሌነ ወኢያይድዑነ ወኢአሐዱ እምኔሆሙ ።

፶፪ ወናሁ አምጻእነ ቍርባነ ለእግዚአብሔር ብእሲ ብእሲ ዘረከበ ሠርጐ ወርቀ በዝግና፣ ወእውቃረ፣ ወኅልቀተ፣ ወሐብላተ ዘዕፍሮ ከመ ታስተሥርዩ በእንቲአነ ቅድመ እግዚአብሔር ።

፶፫ ወነሥኡ ሙሴ ወአልአዛር ካህን ውእተ ወርቀ እምኔሆሙ ወኵሎ ሠርጐ ዘግቡር ።

፶፬ ወኮነ ኵሉ ወርቅ ዘመባእ ዘፈለጡ ለእግዚአብሔር እልፍ ወስሳ ምእት፣ ወሰብዓቱ ምእት ወሐምሳ፣ በሰቅል እምኀበ መላእክተ ዐሠርቱ ምእት ወመላእክተ ምእት ።

የእግዚአብሔርን የድንኳኑን ሥርዓት ለሚጠብቁ ለሌዋውያን ሰጣቸው አለው ። ዘፀ፣ ፲፪ ፷፩ ።

ሙሴና ካህኑ አልአዛርም እግዚአብሔር ሙሴን እንዳዘዘው አደረጉ ።

ወደ ሰልፍ የሄዱ ሰዎች የማረኳቸው የበጎቹ ቍጥር ስሳ ሰባት እልፍ ከአምስት ሺሕ ሆነ ።

ላሞችም ሰባት እልፍ ከሁለት ሺሕ ሆኑ ።

አህዮችም ሰባት እልፍ ከአሥር ሺሕ ሆኑ ።

ከወንድ ያልደረሱ የሴት አካል ያላቸው ሰዎችም ሦስት እልፍ ከሁለት ሺሕ ሆኑ ።

ከበጎችም ቍጥር ወደ ሰልፍ የሄዱ የአርበኞቹ ክፍል እኩሌታ ሠላሳ ሦስት እልፍ ሰባት ሺሕ ከአምስት መቶ ሆነ።

ከበጎች ለእግዚአብሔር የወጣው ዓሥራት ሰባት መቶ ከሰባ አምስት ሆነ ።

ላሞችም፣ ሦስት እልፍ ከስድስት ሺሕ ሆኑ ።

የእግዚአብሔርም ግብሩ (ዓሥራቱ) ሰባ ሁለት ሆነ ።

አህዮችም፣ ሦስት እልፍ ከአምስት መቶ ሆኑ ።

የእግዚአብሔርም ግብሩ ስሳ አንድ ሆነ ።

አእምሮ ያላቸው የተማረኩት ሰዎች (ከሴት ያልደረሱ) እልፍ ከስድስት ሺሕ ሆኑ ። ዘኍ፣ ፲፰ ፰ ።

የእግዚአብሔርም ዐሥራት ሠላሳ ሁለት ሆነ ።

ሙሴም ለእግዚአብሔር ብለው የለዩትን ዓሥራት እግዚአብሔር ሙሴን እንዳዘዘው ለአልአዛር ካህን ሰጠው ።

ከእስራኤል ልጆች እኩሌቶች ወደ ሰልፍ ከሄዱት ሰዎች ሙሴ ያወጣው ይህ ነው ። ዘኍ፣ ፵፩ ፴ ።

ከሠራዊቱ ከበጎች የተገኘው የዚህ እኩሌታ፣ ሠላሳ ሦስት እልፍ ሰባት ሺሕ ከአምስት መቶ ሆነ ።

ላሞችም፣ ሦስት እልፍ ስድስት ሺሕ ናቸው ።

አህዮችም፣ ሦስት እልፍ አምስት መቶ ናቸው ።

ከሴት ያልደረሱ (የወንድ አካል ያላቸው) ሰዎች እልፍ፣ ከስድስት ሺሕ ናቸው ።

ሙሴም ከእስራኤል ልጆች እኩሌታ ከሰዎችም ከከብቶችም ከአምሳ አንዱን ተቀብሎ እግዚአብሔር ሙሴን እንዳዘዘው የእግዚአብሔር ማደሪያ የሆነች የደብተራ ኦሪትን ሥርዓት ለሚጠብቁ ሌዋውያን ሰጣቸው ።

የሺ አለቆች፣ የመቶ አለቆችም ሁሉ ወደ ሙሴ መጥተው እንዲህ አሉት ። ዘፍ፣ ፷፪ ፷፪፣ ሕዝ፣ ፲፯ ፲፪ ።

ብሮችህ ከኛ ጋር የወጉዋቸውን ሰዎች ጌጥ ሸልማት ወሰዱ፣ ከነሱም አንዱ ስንኳ አልነገሩንም ።

አንዱም አንዱም ሰው ያገኘውን እነሆ የወርቁን ጌጣ ጌጥ አምባሩንና ዝርግፉን እንጥልጥሉንና ቀለበቱን ስለኛ በእግዚአብሔር ፊት ኃጢአታችንን ታስተሠርዩልን ዘንድ ለእግዚአብሔር ቍርባን አድርገን አምጥተናል አሉት ።

ሙሴና ካህኑ አልአዛርም ከነዚያ ያንን የወርቁን ጌጣ ጌጥ ሁሉ ተቀበሉ ። ዘፀ፣ ፴ ፲፮፣ ፰ ፲፬ ።

ከመቶ አለቆችና ከሺ አለቆች የተቀበሉት ለእግዚአብሔር ለይተው ያገቡት ወርቁ ሁሉ በሚዛን እልፍ ስድስት ሺሕ ከሰባት መቶ አምሳ ሆነ ።

፶፫ ወእልክቱሰ እደው እለ ፀብኡ አእተዉ ለለርእሶሙ ዘሰለቡ ።

እነዚያ የተዋጉ ሰዎች ግን የዘረፉትን እየራሳቸው አገቡ ።

፶፬ ወነሥኡ ሙሴ ወአልአዛር ካህን ውእተ ወርቀ እምኀበ መላእክተ ዐሠርቱ ምእት ወእምኀበ መላእክተ ምእት ወአብኡ ውስተ ደብተራ መርጡል ተዝካሮሙ ለደቂቀ ሽኤል ።

ካህኑ አልአዛርና ሙሴም ያንን ወርቅ ከሙቶ አለቆችና ከሺ አለቆች ተቀብለው ለእስራኤል ልጆች መታሰቢያ ሊሆን ወደ ደብተራ ኦሪት አገቡ ።

## ምዕራፍ ፴፪ ።

## ምዕራፍ ፴፪ ።

፩ ወበሙ ለደቂቀ ሮቤል ወለደቂቀ ጋድ ብዙኅ እንስሳ ጥቀ ወርእዩዎ ለብሔረ ያዜር ወለብሔረ ገለአድ ከመ ብሔረ እንስሳ ብሔሩ ።

ለጋድ ልጆችና ለሮቤል ልጆች እጅግ ብዙ ከብት ነበራቸው ፤ የገለአድ አገርና የያዜር አገርም አገርነቱ የከብት አገር እንደሆነ አዩተው ።

፪ ወመጽኡ ደቂቀ ሮቤል ወደቂቀ ጋድ ወይቤልዎሙ ለሙሴ ወለአልአዛር ካህን ወለመላእክተ ተዓይን እንዘ ይብሉ ።

የጋድ ልጆችና የሮቤል ልጆች መጥተው ለካህኑ ለአልአዛርና ለሙሴ ለሠራዊቱም አለቆች እንዲህ አሉዋቸው ።

፫ አጣሮታ ወዴቦን ወያዜር ወናምራ ፤ ወሐሴቦን ፤ ወኤልያሌ ፤ ወሴባማ ፤ ወናባው ፤ ወቤያን ፤ ምድር ዘወሀበ እግዚአብሔር ቅድሜሆሙ ለደቂቀ እስራኤል ምድረ እንስሳ እማንቱ ፤ ወብነ ለአግብርቲከ ብዙኅ እንስሳ ።

አጣሮታና ዴቦን ፤ ናምራና ሐሴቦን ፤ ኤልያሌና ሴባማ ፤ ናባውና ቤያን እግዚአብሔር በእስራኤል ልጆች ፊት የሰጠን የከብት አገሮች ናቸው ፤ ለኛ ለባሮችህም ብዙ ከብት አለን አሉዋቸው ።

፬ ወይቤልዎ ለእመ ረከብነ ሞገሰ በቅድሜከ ሀበነ እላንተ በሐውርተ ለአግብርቲከ መክፈልተ ይኩናነ ወኢታዕድወነ ዮርዳኖስ ።

በፊትህ ባለሟልነትን አግኝተን እንደሆነ ፈንታችን ይሆኑን ዘንድ እነዚያን አገሮች ለኛ ለባሮችህ ስጠን ፤ ዮርዳኖስንም አታሻግረን አሉት ።

፭ ወይቤሎሙ ሙሴ ለደቂቀ ሮቤል ወለደቂቀ ጋድ አኅዊክሙ የሐውሩ ይትቃተሉ ወአንትሙሰ ትነብሩ ዝየ ።

ሙሴም የጋድ ልጆችንና የሮቤልን ልጆች ወንድሞቻችሁ ሊዋጉ ይሄዳሉ እናንተ ግን ከዚህ ልትኖሩ ነውን ፤ ።

፮ ለምንት ትገፈትዑ ልበሙ ለደቂቀ እስራኤል ከመ ኢይሑሩ ውስተ ምድር ዘይሁበሙ እግዚአብሔር ።

እግዚአብሔር ወደ ሚሰጣቸው አገር እንዳይሄዱ የእስራኤልን ልጆች ልቡና ለምን ታጠፉታላችሁ ፤ ።

፯ አኮኑ ከመዝ ገብሩ አበዊክሙ አመ ፈነውክዎሙ እምቃዴስ በርኔ ከመ ይርአይዋ ለይእቲ ምድር ።

ያችን አገር ያዩዋት ዘንድ ወደ ቃዴስ በርኔ በላክኋቸው ጊዜ አባቶቻችሁ እንዲህ ያደረጉ አይደለምን ፤ ።

፰ ወዐርጉ ኀበ ቈላተ ዐጽቅ ከመ ይነጽርዋ ለይእቲ ምድር ወሜጥዎ ለልበሙ ለደቂቀ እስራኤል ከመ ኢይበኡ ውስተ ይእቲ ምድር ዘይሁበሙ እግዚአብሔር ።

ያችን አገር ያዩዋት ዘንድ የወይን ዘለላ ወዳለበት ቈላ ወጥተው እግዚአብሔር ወደሚሰጣቸው ወደዚያች አገር እንዳይገቡ የእስራኤልን ልጆች ልቡና ለወጡ ።

፱ ወተምዐ መዐተ እግዚአብሔር በይእቲ ዕለት ወመሐለ እንዘ ይብል ፤ ከመ ኢይበውእዋ ለይእቲ ምድር እደው እለ ወፅኡ እምግብጽ ዘእምዕሥራ ዓም ወላዕሉ ።

እግዚአብሔር በዚያች ቀን ቍጣን ተቈጣ ፤ ከሃያ ዓመት ጀምሮ ከዚያም በላይ ያሉ ከግብጽ የወጡ ሰዎች ያችን ምድር አያዩዋትም ብሎ ማለ ። ዘኍ ፲፫ ፴፫ ።

፲ ለምድር ዘመሐልኩ ለአብርሃም ወለይስሐቅ ወለያዕቆብ እስመ ኢተለዉ ድኅሬሁ ዘእንበለ ካሌብ ወልደ ዮፎኒ ዘተፈልጠ ወሆሴዕ ወልደ ነዌ እስመ ተለዉ ድኅሬሁ ለእግዚአብሔር ።

ግብራቸው ከተለየ ከዮፎኒ ልጅ ከካሌብና ከነዌ ልጅ ከሆሴዕ በቀር እግዚአብሔርን (በሃይማኖት) አልተከተሉትምና ለአብርሃም ለይስሐቅና ለያዕቆብ የማልሁላቸውን ያችን ምድር እንዳይገቡባት ብሎ ማለ ፤ ካሌብና ሆሴዕ ግን እግዚአብሔርን ተከትለዉታልና ከነዚህ በቀር ።

፲፩ ወተምዐ መዐተ እግዚአብሔር ላዕለ እስራኤል ወአዔሎሙ ውስተ ገዳም አርብዓ ዓመተ እስከ ጠፍኡ ኵሉ ትውልድ እለ ገብሩ እኪተ ቅድመ እግዚአብሔር ።

በእግዚአብሔር ፊት ክፉ ሥራ የሠሩት ትውልድ ሁሉ እስኪጠፉ ድረስ እግዚአብሔር በእስራኤል ላይ ተቈጥቶ በምድረ በዳ አርባ ዘመን አዞራቸው ።

፲፪ ወናሁ ተንሣእክሙ ህየንተ አበዊክሙ በማዕሴተ ሰብእ ኃጥአን ከመ ትወስኩ ዓዲ መዐተ በዲበ መዐቱ ለእግዚአብሔር ላዕለ እስራኤል ።

በእግዚአብሔር መዓት ላይ ዳግመኛ በእስራኤል ላይ መዓትን ትጨምሩ ዘንድ ኃጥአን በሚሆኑ ሰዎች በደል እነሆ ስለ አባቶቻችሁ ፈንታ ተነሣችሁ ፤ ።

፲፫ እስመ ኀደግምዎ ዓዲ ትደግሙ ኀዲጎቶ በገዳም ወትኤብሱ ላዕለ ኵሉ ዘቲ ትዕይንት ።

እግዚአብሔርን ትታችሁታልና ዳግመኛም በምድረ በዳ ተዋችሁት ፤ በዚህች ወገን ላይም ትበድላላችሁ ።

፲፬ ወቀርቡ ኀቤሁ ወይቤልዎ ንንድቅ ዝየ አዕጻዳተ ለአንስሳነ ወአህጉረ ለደቂቅነ ።

ወደርሱም ቀርበው ከዚህ ለበጎቻችን ማደሪያ እንሥራ ለልጆቻችንም አገር እናቅና አሉት ።

፲፭ ወንሕነሰ ምስለ ንዋየ ሐቅልነ ፍጽመ ነሐውር ቅድሜሆሙ ለደቂቀ እስራኤል እስከ ናበጽሖሙ ውስተ መካኖሙ ።

እኛ ግን ወደ በታቸው እስክናደርሳቸው ድረስ በእስራኤል ልጆች ፊት ጦራችንን ይዘን በፊት እንሄዳለን ።

፲፮ ወይነብሩ ደቂቅነ ውስተ አህጉር እለ ቦቶን ቅጽር በእንተ ሰብአ ብሔር ።

በአገር ስላሉም ሰዎች ቅጽር ባላቸው አገሮች ልጆቻችን ይቀመጡ ። ዘኍ፡ ፴፩ ፫፡ ኢያ፡ ፬ ፲፪ ።

፲፯ ወኢንገብእ ውስተ አብያቲነ እስከ ይትከፈሉ እስራኤል ርስቶሙ ዘዘዚአሆሙ ።

እስራኤል የየራሳቸውን ርስት እስኪከፈሉ ድረስ ወደ ቤቶቻችን አንመለስም ። ኢያ፡ ፳፪ ፬ ።

፲፰ ወኢንትከፈሎሙ እንከ እማዕዶተ ዮርዳኖስ ፤ ወከሐከ እምኔሁ እስመ ነሣእነ ክፍለነ እማዕዶተ ዮርዳኖስ ዘመንገለ ጽባሕ ።

በምሥራቅ በኩል በዮርዳኖስ ማዶ ከዚያም ወዲያ እንግዲህ አንከፈላቸውም አሉት ። ኢያ፡ ፩ ፲፬ ።

፲፱ ወይቤሎሙ ሙሴ ለእመ ገበርክሙ በከመ ትቤሉ ወሐርክሙ ምስለ ንዋየ ሐቅልክሙ ቅድመ እግዚአብሔር ውስተ ፀብእ ።

ሙሴም እንዳላችሁት ከደረጋችሁ ጋሻ ጦራችሁን ይዛችሁ በእግዚአብሔር ፊት ወደ ጦርነት ትሄዳላችሁ ። ዘዳ፡ ፫ ፲፰ ።

፳ ወየዐድውክሙ ኵልክሙ ምስለ ንዋየ ሐቅልክሙ ዮርዳኖስ ቅድመ እግዚአብሔር ።

ጋሻ ጦራችሁን ይዛችሁ በእግዚአብሔር ፊት ዮርዳኖስን ከተሻገራችሁ ። ዘፀ፡ ፲፭ ፱፡ ኢያ፡ ፩ ፲፬ ።

፳፩ ወእምድኅረ ዝንቱ ትገብኡ ወንጹሓነ ትከውኑ ቅድመ እግዚአብሔር ወእምእስራኤልኒ ወትከውን ለክሙ ዛቲ ምድር መክፈልተክሙ ቅድመ እግዚአብሔር ።

ከዚያም በኋላ ተመልሳችሁ እግዚአብሔርን ከመበደል እስራኤልንም ከማሳዘን ንጹሐን ትሆናላችሁ ፤ ያችም አገር በእግዚአብሔር ፊት ዕድል ፈንታችሁ ትሆናለች ።

፳፪ ወለእመሰ ኢገበርክሙ ከመዝ ትጌግዩ ቅድመ እግዚአብሔር ፤ ወአመ ረከበተክሙ እኪት ተአምርዋ ለአበሳክሙ ።

እንደዚህ ካላደረጋችሁ ግን በእግዚአብሔር ፊት ትበድላላችሁ ፤ ያችም መከራ ባገኛችሁ ጊዜ ኃጢአታችሁን ታውቋታላችሁ ። ዘፍ፡ ፵፬ ፲፮፡ ኢሳ፡ ፶፱ ፲፪ ።

፳፫ ወንድቁ ለክሙ አህጉረ ለደቂቅክሙ ፤ ወአፀዳተ ለእንስሳክሙ ፤ ወግበሩ በከመ ወፅአ እምአፉክሙ ።

ለልጆቻችሁ አምባ ለከብቶቻችሁም ዘለላ ሥሩ ፤ ከአፋችሁም እንደወጣ አድርጉ ።

፳፬ ወይቤልዎ ደቂቀ ሮቤል ወደቂቀ ጋድ ለሙሴ ንሕነ አግብርቲከ ንገብር በከመ አዘዝከነ እግዚእነ ።

ሙሴን የጋድ ልጆችና የሮቤል ልጆች እና ባሮችህ አንተ ጌታችን እንዳዘዝከን እናደርጋለን አሉት ።

፳፭ ደቂቅነ ወአንስትያነ ይንበሩ ውስተ አህጉረ ገለአድ ወኵሉ እንስሳነ ።

ሚስቶቻችንና ልጆቻችንም በገለአድ አምባዎች ሁሉ ይቀመጡ ።

፳፮ ወንሕነሰ ነሐውር ኵልነ ምስለ ንዋየ ሐቅልነ ተረሲየነ ቅድመ እግዚአብሔር ውስተ ፀብእ በከመ ትቤለነ እግዚእነ ።

እኛ ግን ሁላችን ጋሻ ጦራችንን ይዘን አንተ ጌታችን እንዳልከን በእግዚአብሔር ፊት ተጸርረን ወደ ጦርነት እንሄዳለን አሉት ። ዘኍ፡ ፴፩ ፭ ።

፳፯ ወአዘዞሙ ሙሴ ለአልአዛር ካህን ወለኢያሱ ወልደ ነዌ ፤ ወለመላእክተ አበዊሆሙ ለነገደ እስራኤል ።

ሙሴም የነዌ ልጅ ኢያሱንና ካህኑ አልአዛርን የእስራኤል ነገድ የሚሆኑ የአባቶቻቸውን አለቆች አዘዛቸው ።

፳፰ ወይቤሎሙ ለእመ ዐደዉ ምስሌክሙ ደቂቀ ሮቤል ወደቂቀ ጋድ ዮርዳኖስ ኵሎሙ ምስለ ተዋየ ሐቅሎሙ ውስተ ፀብእ ቅድመ እግዚአብሔር ዛተ ምድረ ገለአድ እንተ ቅድሜክሙ ትሁብዎሙ መክፈልቶሙ ።

የጋድ ልጆችና የሮቤል ልጆች ከናንተ ጋራ ሁላቸው ጋሻ ጦራቸውን ይዘው በእግዚአብሔር ፊት ዮርዳኖስን ቢሻገሩ በፊታችሁ የምታዩዋት ይህችን የገለአድ አገር ፈንታቸውን ስጡዋቸው ። ዘኍ፡ ፳፯ ፲፰ ።

፳፱ ወለእመሰ ኢዐደዉ ምስሌክሙ ውስተ ፀብእ በንዋየ ሐቅሎሙ ቅድመ እግዚአብሔር አግዕዙ ደቂቆሙ ወአንስትያሆሙ ወእንስሳሆሙ ቅድሜክሙ ውስተ ምድረ ከነዓን ።

ከናንተ ጋር ጋሻ ጦራቸውን ይዘው በእግዚአብሔር ፊት ወደ ጦርነት ባይሄዱ ግን ሚስቶቻቸውንና ልጆቻቸውን ከብቶቻቸውንም ሁሉ ወደ ፊታችሁ ወደ ከነዓን ምድር ንዱዋቸው ።

፴ ወአውሥኡ ደቂቀ ሮቤል ወደቂቀ ጋድ ወይቤሉ ኵሎ ዘይቤለነ እግዚእነ ከማሁ ንገብር ንሕነ ።

የጋድ ልጆችና የሮቤል ልጆች ጌታችን ያለንን ሁሉ እኛ እናደርጋለን አሉ ።

፴፩ ወንዐዱ በንዋየ ሐቅልነ ቅድመ እግዚአብሔር ውስተ ምድረ ከነዓን ወሀቡነ መክፈልተነ ውስተ ማዕዶተ ዮርዳኖስ ።

ጋሻ ጦራችንን ይዘን በእግዚአብሔር ፊት ወደ ከነዓን እንሻገራለን ፤ በዮርዳኖስ ማዶ ፈንታችንን ስጡን ብለው መለሱ ።

፴፪ ወወሀቦሙ ሙሴ ለደቂቀ ጋድ ወለደቂቀ ሮቤል ወለመንፈቀ ነገደ ምናሴ ወልደ ዮሴፍ መንግሥተ ሴዎን ንጉሠ አሞሬዎን ፤ ወመንግሥተ አግ ንጉሠ ባሳን ምድሮሙ ወአህጉሪሆሙ ምስለ አድባሪሆሙ ወአህጉረ ዘውስተ ምድር ዘዓውዶሙ ።

ለጋድ ልጆችና ለሮቤል ልጆች ለዮሴፍም ልጅ ለምናሴ ነገድ እኩሌታም የባሳን ንጉሥ የአግን ግዛትና የአሞሬዎንን ንጉሥ የሴዎንን ግዛት ፤ አምባቸውንና አገራቸውን ከአውራጃዎቻቸው ጋር በዙርያቸው ምድር ያሉ መንደሮቻቸውንም ሰጧቸው ። ዘዳ፡ ፫ ፲፪ - ፲፯ ።

፴፫ ወነደቁ ደቂቀ ጋድ ዴቦንሃ ፤ ወአጣሮት ወአሮኤር ፤ ወሰፋን ወያዜር ።

የጋድም ልጆች አጣሮትንና ዴቦንን ሰፋንና አሮኤርን ያዜርንም ። ዘኍ፡ ፴፪ ፫፡ ፳፩ ፬ ።

፴፬ ወናምራ ወቤታራን ሰብዓተ አህጉረ ጽኑዐተ ወአንጎ ምን ወአዕፃዳተ አባግዕ ።
፴፭ ወደቂቀ ሮቤል ነደቁ ሐሴቦንሃ ወእልያሌ ወቀርያቴም ወቤኤልሜዎን ወቀጽሮን ወሴባማ ።
፴፮ ወሰመይዎን በበአስማቲሆን ለአህጉር ዘነደቁ ።
፴፯ ወሖረ ገለአድ ወልደ ማኪር ወልደ ምናሴ ወነሥአ ለገለዓድ ወአጥፍአሙ ለአሞሬዎን እለ ይነብሩ ውስቴታ ።
፴፰ ወወሀበ ሙሴ ለማኪር ወልደ ምናሴ ገለዓድሃ ፡ ወነበረ ውስቴታ ።
፴፱ ወኢያዕር ወልደ ምናሴ ሖረ ወነሥአ አዕፃዳቲሆሙ ወሰመይዎን አዕፃዳተ ኢያዕር ።
፵ ወሖረ ናባው ወነሥአ ለቃናት ወለአዕፃዳቲሃ ወሰመያ ናባት በስመ ዚአሁ ።

ምዕራፍ ፴፫ ።

፩ ወዝንቱ ውእቱ ማኅደሪሆሙ ለደቂቀ እስራኤል እምዘወፅኡ እምግብጽ ምስለ ኀይሎሙ በእደ ሙሴ ወአሮን ።
፪ ወጸሐፈ ሙሴ ማኅደሪሆሙ እምጣነ ግዕዙ በቃለ እግዚአብሔር ፡ ወዝንቱ ውእቱ ማኅደሪሆሙ ዘግዕዙ ።
፫ ወግዕዙ እምራምሴ በቀዳሚ ወርኅ አመ ዐሡሩ ወኃሙሱ ለቀዳሚ ወርኅ በሳኒታ ፋሲካ ወፅኡ ደቂቀ እስራኤል በእድ ልዕልት ፡ በቅድመ ኵሉ ግብጽ ።
፬ ወግብጽሰ ይቀብሩ ምውቶሙ ኵሎ ዘቀተለ እግዚአብሔር ፡ ኵሎ በኵሩ ለምድረ ግብጽ ወላዕለ አማልክቲሆሙኒ ገብረ እግዚአብሔር በቀለ ።
፭ ወግዕዙ ደቂቀ እስራኤል እምራምሴ ወኀደሩ ውስተ ሰቆት ።
፮ ወግዕዙ እምነ ሰቆት ወኀደሩ ውስተ ኁታን ወአሐዱ ኅብረ በድው ውእቱ ።
፯ ወግዕዙ እምኁታን ወኀደሩ ኀበ አፉሁ ለኤሮት ዘቅድሙ ብዔልሴፎር ወቅድመ መግደሎ ።
፰ ወግዕዙ እምቅድመ መግደሎ ዘኤሮት ወዐደዉ እንተ ማእከለ ባሕር ውስተ ገዳም ወሖሩ ሠለስ ዕለተ ውስተ መገዳ ኤታም ወኀደሩ ውስተ ምረት ።
፱ ወግዕዙ እምረት ወበጽሑ ውስተ ኤሌም ወሀለዉ ውስተ ኤሌም ዐሠርቱ ወክልኤቱ አንቅዕተ ማይ ፡ ወሰብዓ በቀልተ ተመርት ወኀደሩ ህየ ኀበ ማይ ።
፲ ወግዕዙ እምኤሌም ወኀደሩ ውስተ ባሕረ ኤርትራ ።
፲፩ ወግዕዙ እምባሕረ ኤርትራ ወኀደሩ ውስተ ገዳም ዘሲን
፲፪ ወግዕዙ እምገዳም ዘሲን ወኀደሩ ውስተ ራፋቃ ።
፲፫ ወግዕዙ እምራፋቃ ወኀደሩ ውስተ ኤሉስ ።
፲፬ ወግዕዙ እምኤሉስ ወኀደሩ ውስተ ራፊድን ፡ ወአልበ ህየ ማይ ዘይሰትዩ ሕዝብ ።
፲፭ ወግዕዙ እምራፊድን ወኀደሩ ውስተ ገዳም ዘሲና ።

ናምራንና ቤታራንን ጽኑዓን የሆኑ እነዚህን ሰባቱ አገሮች አስፋፍተው የበጎችን ማደሪያዎች ቀጸሩ ።
የሮቤልም ልጆች እልያሌንና ሐሴቦንን ቤኤልሚዎንንና ቀርያቴምን ፡ ቀጽሮንንና ሴባማን ቀጸሩ ።
የቀጸሩዋቸውንም አገሮች በየስማቸው ጠሩዋቸው ።
የምናሴ ልጅ የማኪር ልጅ ገለአድም ሄዶ ገለዓድን እጅ አደረጋት ፡ በውስጧ የሚኖሩ አሞሬዎንንም አጠፉቸው ። ዘፍ ፶ ፳፫ ።
ሙሴም ለምናሴ ልጅ ለማኪር ልጅ ገለዓድን ሰጠው በርሷም ኖረ ። ዘዳ ፫ ፲፫ - ፲፭ ፡ ኢያ ፲፫ ፴፩ ።
የምናሴ ልጅ ኢያዕርም ሄዶ አውራጃዎቻቸውን ሁሉ እጅ አደረገ ፡ አውራጃዎቹንም የኢያዕር አውራጃዎች አሏቸው ። ዘዳ ፫ ፲፬ ፡ ፩ ዜና ፪ ፳፩ ።
ናባውም ሄዶ ቃናትን ከአውራጃዎቿ ጋር እጅ አደረጋት ፡ ስሟንም በስሙ ናባት አላት ። ዘኁ ፳፩ ፳፭ ።

ምዕራፍ ፴፫ ።

በሙሴና በአሮን መሪነት ከሠራዊቶቻቸው ጋር ከግብጽ ከወጡ በኋላ የእስራኤል ልጆች ሰፍረው ያደሩበት ማደሪያቸው ይህ ነው ።
ሙሴም በእግዚአብሔር ፈቃድ እንደ ተጓዙና በተጓዙት ልክ ሰፍረው ያደሩበት ማደሪያቸውን ጻፈ ፡ ተጉዘው ያደሩበት ሰፈራቸው ይህ ነው ።
በመጀመሪያው ወር ከራምሴ ተጓዙ ፡ ሚያዝያ በባተ በዓሥራ አምስት ቀን በፋሲካ ማግስት የእስራኤል ልጆች በጽኑ ሥልጣን የግብጽ ሰዎች እያዩዋቸው ወጡ ።
የግብጽ ሰዎች ግን እግዚአብሔር በግብጽ አገር የገደለውን በኵር በኵሩን ሁሉ ሬሳቸውን ይቀብሩ ነበር ፡ እግዚአብሔር በጣኦቶቻቸው በቀልን አደረገ ።
የእስራኤልም ልጆች ከራምሴ ተጕዘው በሰቆት አደሩ ። ዘፀ ፲፪ ፴፯ ።
ከሰቆትም ተጕዘው በኁታን አደሩ ፡ ይኸውም አንድ ወገኑ ምድረ በዳ ነው ። ዘፀ ፲፫ ፳ ።
ከኁታንም ተጕዘው በመግደሎና በብኤል ሴፎር አንጻር ባለ በኤሮት አፋፍ አደሩ ። ዘፀ ፲፬ ፱ ።
ከኤሮት ክፍል ከምትሆን ከመግደሎን ተጕዘውም በባሕር መካከል ወደ ምድረ በዳ ተሻገሩ ፡ ወደ ኤታም ምድረ በዳ ሦስት ቀን ተጕዘው በምረት አደሩ ።
ከምረትም ተጕዘው ወደ ኤሌም ደረሱ ፡ በኤሌምም ዓሥራ ሁለት የውኃ ምንጮች ሰባ የተምር ዘንባባ ነበሩ ፡ በዚያም በውኃው ዘንድ አደሩ ። ዘፀ ፲፭ ፳፯ ።
ከኤሌምም ተጕዘው በኤርትራ ባሕር ዳር አደሩ ።
ከኤርትራ ባሕርም ተጕዘው በሲና ምድረ በዳ አደሩ ።
ከሲና ምድረ በዳም ተጕዘው በራፋቃ አደሩ ።
ከራፋቃም ተጕዘው በኤሉስ አደሩ ።
ከኤሉስም ተጕዘው በራፊድን አደሩ ፡ በዚያም ሕዝቡ የሚጠጡት ውኃ አልነበረም ። ዘፀ ፲፯ ፩ ።
ከራፊድንም ተጕዘው በሲና ምድረ በዳ አደሩ ።

| | | |
|---|---|---|
| ወግዕዙ እምገዳም ዘሲና ፡ ወኀደሩ ውስተ መቃብረ ፍትወት ። | ፲፮ | ከሲና ምድረ በዳም ተጕዘው በምኞት መቃብር (እስራኤል ሥጋ ተመኝተው ወደ ተቀበሩበት) መቃብር ሰፈሩ። |
| ወግዕዙ እመቃብረ ፍትወት ወኀደሩ ውስተ አሴሮት ። | ፲፯ | ከምኞት መቃብርም ተጕዘው በአሴሮት ሰፈሩ ። |
| ወግዕዙ እምአሴሮት ወኀደሩ ውስተ ራታማ ። | ፲፰ | ከአሴሮትም ተጕዘው በራታማ አደሩ ። ዘኍ፡ ፲፪ ፲፮። |
| ወግዕዙ እምራታማ ወኀደሩ ውስተ ሬሞት ዘፋሬስ ። | ፲፱ | ከራታማም ተጕዘው የፋሬስ ዕጣ በምትሆን በሬሞት አደሩ ። |
| ወግዕዙ እምነ ሬሞት ዘፋሬስ ወኀደሩ ውስተ ሌበና ። | ፳ | የፋሬስ ዕጣ ከምትሆን ከሬሞትም ተጕዘው በሌበና አደሩ ። |
| ወግዕዙ እምነ ሌበና ወኀደሩ ውስተ ሊስ ። | ፳፩ | ከሊበናም ተጕዘው በሊስ አደሩ ። |
| ወግዕዙ እምነ ሊስ ወኀደሩ ውስተ መቄዶት ። | ፳፪ | ከሌስም ተጕዘው በመቄዶት አደሩ ። |
| ወግዕዙ እምነ መቄዶት ወኀደሩ ውስተ አርሳፍር ። | ፳፫ | ከመቄዶትም ተጕዘው በአርሳፍር አደሩ ። |
| ወግዕዙ እምነ አርሳፍር ወኀደሩ ውስተ ከሬዳ ። | ፳፬ | ከአርሳፍር ተጕዘው ወደ ከሬዳ አደሩ ። |
| ወግዕዙ እምነ ከሬዳ ወኀደሩ ውስተ መቄዶት ። | ፳፭ | ከከሬዳም ተጕዘው በመቄዶት ሰፈሩ ። |
| ወግዕዙ እምነ መቄዶት ወኀደሩ ውስተ ቀጣዓት ። | ፳፮ | ከመቄታም ተጕዘው በቀጠዓት (በቀጥያት) አደሩ ። |
| ወግዕዙ እምነ ቀጣዓት ወኀደሩ ውስተ ተሬት ። | ፳፯ | ከቀጥያትም ተጕዘው በተሬት ሰፈሩ ። |
| ወግዕዙ እምነ ተሬት ወኀደሩ ውስተ መቴቃ ። | ፳፰ | ከተሬትም ተጕዘው በመቴቃ አደሩ ። |
| ወግዕዙ እምነ መቴቃ ወኀደሩ ውስተ ኤሴምና ። | ፳፱ | ከመቴቃም ተጕዘው በኤሴምና ሰፈሩ ። |
| ወግዕዙ እምነ ኤሴምና ወኀደሩ ውስተ መሱሩት ። | ፴ | ከኤሴምና ተጕዘው በመሱሩት አደሩ ። ዘዳ፡ ፲ ፮ ። |
| ወግዕዙ እምነ መሱሩት ወኀደሩ ውስተ በንያቅን ። | ፴፩ | ከመሱሩትም ተጕዘው በበንያቅን አደሩ ። |
| ወግዕዙ እምነ በንያቅን ወኀደሩ ውስተ ገድገድ ። | ፴፪ | ከበንያቅንም ተጕዘው በገድገድ አደሩ ። |
| ወግዕዙ እምገድገድ ወኀደሩ ውስተ ኤጤቤት ። | ፴፫ | ከገድገድም ተጕዘው በኤጤቤት አደሩ ። |
| ወግዕዙ እምነ ኤጤቤት ወኀደሩ ውስተ ኤብሮና ። | ፴፬ | ከኤጤቤትም ተጕዘው በኤብሮና አደሩ ። |
| ወግዕዙ እምነ ኤብሮና ወኀደሩ ውስተ ጋስዮን ጋቤር ። | ፴፭ | ከኤብሮናም ተጕዘው በጋስዮን ጋቤር አደሩ ። |
| ወግዕዙ እምጋስዮን ጋቤር ወኀደሩ ወስተ ገዳም ዘዪን ። | ፴፮ | ከጋስዮን ጋቤር ተጕዘው በሲና ምድረ በዳ አደሩ ። |
| ወግዕዙ እምገዳም ዘዪን ወኀደሩ ውስተ ገዳም ዘፋራን ዘውእቱ ቃዴስ ። | ፴፯ | ከሲና ምድረ በዳም ተጕዘው በፋራን ምድረ በዳ አደሩ ፡ ይኸውም ቃዴስ ነው ። ዘኍ፡ ፳ ፳፪ ፡ ፳፩ ፩ ። |
| ወግዕዙ እምቃዴስ ወኀደሩ ውስተ ደብረ ሆር ዘገበው ለምድረ ኤዶም ። | ፴፰ | ከቃዴስም ተጕዘው በኤዶም ምድር ጐን ባለ በሆር ተራራ አደሩ ። ዘኍ፡ ፳ ፳፩ ፡ ዘዳ፡ ፴፪ ፶ ። |
| ወዐርገ አሮን ካህን በትእዛዘ እግዚአብሔር ወሞተ በሀየ አመ አርበዓ ዓም እምዘወፅኡ ደቂቀ እስራኤል እምግብጽ በኃምስ ወርኅ አመ ሠርቀ ወርኅ ። | ፴፱ | ካህኑ አሮን በእግዚአብሔር ትእዛዝ ወጥቶ የእስራኤል ልጆች ከግብጽ በወጡ በአርባ ዓመት በአምስተኛው ወር የነሐሴ መባቻ በዚያ በደብረ ሆር ሞተ ። |
| ወዓመቲሁ ለአሮን አመ ሞተ በደብረ ሆር ምእት ወዕሥራ ወሠለስቱ ዓመት ። | ፵ | በደብረ ሆር በሞተ ጊዜ የአሮን ዘመኑ ፡ መቶ ሃያ ሦስት ነበረ ። ዘኍ፡ ፳፬ ፯ ። |
| ወሰምዐ ከነአን ንጉሠ አራድ እንዘ ይነብር ውስተ ምድረ ከነአን አመ ይበውኡ ደቂቀ እስራኤል ። | ፵፩ | የአራድ ንጉሥ ከነዓንም በከነዓን ተቀምጦ ሳለ የእስራኤልን ልጆች መምጣት ሰማ ። ዘኍ፡ ፳፩ ፩ ። |
| ወግዕዙ እምደብረ ሆር ወኀደሩ ውስተ ሴልሞና ። | ፵፪ | ከደብረ ሆርም ተጕዘው በሴልሞና አደሩ ። |
| ወግዕዙ እምነ ሴልሞና ወኀደሩ ውስተ ፌኖ ። | ፵፫ | ከሴልሞናም ተጕዘው በፌኖ አደሩ ። |
| ወግዕዙ እምነ ፌኖ ወኀደሩ ውስተ አቦት ። | ፵፬ | ከፌኖም ተጕዘው በአቦት ሰፈሩ ። ዘኍ፡ ፴፫ ፵፯ ። |
| ወግዕዙ እምአቦት ወኀደሩ ውስተ ጋይ እንተ ማዕዶተ ደወሎሙ ለሞዓብ ። | ፵፭ | ከአቦትም ተጕዘው በሞዓብ ዳርቻ ማዶ ባለች በጋይ አደሩ ። ዘኍ፡ ፳፩ ፴ ። |
| ወግዕዙ እምነ ጋይ ወኀደሩ ውስተ ዴቦን ዘጋድ ። | ፵፮ | ከጋይም ተጕዘው የጋድ ዕጣ በምትሆን በዴቦን አደሩ። |
| ወግዕዙ እምዴቦን ዘጋድ ወኀደሩ ውስተ ጌልሞን ዘዴብላቴን ። | ፵፯ | ከዴቦን ተጕዘው የዴብላቴን ክፍል በምትሆን በጌልሞን አደሩ ። ዘዳ፡ ፴፪ ፵፱ ። |
| ወግዕዙ እምነ ጌልሞን ዘዴብላቴን ወኀደሩ ውስተ አድዋለ አባርም ዘአንጻረ ናባው ። | ፵፰ | ከዴብላቴን ክፍል ከምትሆን ከጌልሞንም ተጕዘው በናባው አንጻር ባለች በአባርም ተራሮች አደሩ ። |
| ወግዕዙ እምአድባረ አባርም ዘአንጻረ ናባው ወኀደሩ ውስተ ዐረቢሃ ለሞዓብ ኀበ ዮርዳኖስ ዘመንገለ ኢያሪኮ ፡ ወኀደሩ ውስተ ዮርዳኖስ ማእከለ አሲሞት እስከ አቤልሳጢም ። | ፵፱ | ከናባው አንጻር ባለች ከአባርም ተራሮች ተጕዘው በዮርዳኖስ ማዶ በኢያሪኮ አንጻር በሞዓብ ግራ በኩል አደሩ ፡ በአሲሞትም መካከል እስከ አቤልሳጢም ድረስ አደሩ ። ዘኍ፡ ፳፪ ፩ ። |

፶ ወነበበ እግዚአብሔር ለሙሴ በዐረቢሃ ለሞዓብ በኀበ ዮርዳኖስ ዘመንገለ ኢያሪኮ ወይቤሎ ፣ ንግሮሙ ለደቂቀ እስራኤል ወበሎሙ ፣ ናሁ ተዐድዉ አንትሙ ዮርዳኖስ ውስተ ምድረ ከናዓን ።

፶፩ ወአጥፍእዎሙ ለኵሎሙ እለ ይነብሩ ውስተ ይእቲ ምድር እምቅድመ ገጽክሙ ወደምስስ ግብሮሙ ወኵሉ አማልክቲሆሙ አጥፍኡ ወኵሉ አምሳሊሆሙ አሰስሉ ።

፶፪ ወደምስስዎሙ ለእለ ይነብሩ ውስተ ይእቲ ምድር ወንበሩ ውስቴታ ፣ እስመ ለክሙ ወሀብኩክሙ ምድሮሙ ርስተ ።

፶፫ ወተዋረስዋ ለይእቲ ምድር ወተከፈልዋ በበነገድክሙ ለእለ ይበዝኁ አብዝኁ ሎሙ መክፈልቶሙ ፣ ወለእለ ይውኅዱ አውኅዱ ሎሙ መክፈልቶሙ ፣ ወለለዘበጽሖ በስሙ ይኩኖ ሎቱ ህየ በበነገድክሙ ወበበአብያተ አበዊክሙ ተከፈልዋ ።

፶፬ ወለእመሰ ኢያጥፋእክምዎሙ ለእለ ይነብሩ ውስተ ይእቲ ምድር እምቅድመ ገጽክሙ ይከውኑክሙ እለ አትረፍክሙ አሥዋከ ለአዕይንቲክሙ ፣ ወአሜከላ ለገበዋቲክሙ ወይፃረሩክሙ ፣ በውስተ ምድር እንተ ውስቴታ ትነብሩ አንትሙ ።

፶፭ ወዝክተ ዘሐለይኩ ከመ እግበር ላዕሌሆሙ እገብር ላዕሌክሙ ።

ምዕራፍ ፴፬ ።

፩ ወነበበ እግዚአብሔር ለሙሴ ወይቤሎ ፣ እዝዞሙ ለደቂቀ እስራኤል ወበሎሙ ናሁ ትበውኡ ውስተ ምድረ ከናአን አንትሙ ወርስትክሙ ይእቲ ለክሙ ምስለ አድዋሊሃ ።

፪ ወይኩንክሙ ገበሃ ዘመንገለ ገበሃ ለአዜብ እምገዳም ዘጺን እንተ መአንዝ ኤዶም እምነ ገበሃ ለባሕረ ኤሌቄ ዘመንገለ ጽባሕ ።

፫ ወየዐውድ ደወላ ለአዜብ እምዓቀበ አቅራበን ወይበጽሕ እስከ ኤናቅ ወይከውን ሞፃእቱ ለዘመንገለ አዜብ ቃዴስ ዘበርኔ ወይበውእ ውስተ አህጉረ አራድ ወይወፅእ እንተ አሴሞና ።

፬ ወየዐውድ ደወሉ እምአሴሞና ፈለገ ግብጽ ወይከውን ወሰኑ ባሕር ።

፭ ወደወልክሙኒ ዘመንገለ ባሕር ትኩንክሙ ባሕር ዐቢይ ወሰንክሙ ወዝንቱ ውእቱ ወሰንክሙ ዘመንገለ ባሕር ።

፮ ወደወልክሙኒ ዘመንገለ መስዕ እምባሕር ዐቢይ እንተ መንገለ ደብር ይከውን ለክሙ ።

፯ ወእምደብር እስከ ደብር ይከውን ለክሙ ፣ ወይበጽሕ እስከ ኤማት ወይከውን ሞፃእቱ አርሴናይን ዘሴፋማ ፣ ወበዝንቱ ይኩንክሙ ወሰንክሙ ዘመንገለ መስዕ ።

፰ ወደወልክሙኒ ዘመንገለ ጽባሕ እምአርሴናይን ዘሴፋማ ወይወርድ ደወልክሙ እምሴፋማ እስከ አርፌላ ።

፱ ወይትራከብ በዘበነ ባሕረ ከኔሬት እምጽባሕ ።

እነሆ ወደ ከነዓን ለመሄድ ዮርዳኖስን ትሻገራላችሁ ብለህ ለእስራኤል ልጆች ንገራቸው ብሎ በዮርዳኖስ ማዶ በኢያሪኮ አንጻር ባለች በሞዓብ ግራ እግዚአብሔር ለሙሴ ነገረው ። ዘዳ፡ ፱ ፩ ፣ ኢያ፡ ፫ ፲፯ ።

በዚያች አገር የሚኖሩትን ሰዎች ሁሉ ከፊታችሁ አጥፏቸው ፣ ሥራቸውንም አጥፉ ፣ ጣኦቶቻቸውንም ሁሉ አጥፉ ፣ ምስሎቻቸውንም ሁሉ አርቁ ። ዘኁ፡ ፴፪ ፳፩ ።

ምድራቸውን ርስት አድርጌ ለናንተ ሰጥቻችኋለሁና በዚያች አገር የሚኖሩትን ሰዎች አጥፍታችሁ በዚ ኑሩ ። ዘፀ፡ ፲፭ ፱ ፣ ፳፫ - ፳፬ ፣ ዘኁ፡ ፴፫ ፶፪ ።

ያችን ምድር ወርሳችሁ በየነገዳችሁ ተከፈሏት ፣ ለብዙዎቹ ፈንታቸውን አብዙላቸው ፤ ለሚያንሱትም ፈንታቸውን አሳንሱላቸው ፤ ለየደረሰው በስሙ ይጠራበት ፤ በየነገዳችሁ በየአባቶቻችሁ ወገኖች ተከፈሏት ።

በዚያች አገር የሚኖሩትን ሰዎች ከፊታችሁ ባታጠፉቋቸው ግን ያስቀራችኋቸው ሰዎች ለዓይናችሁ እሾኽ ለጐኖቻችሁ አሜከላ ይሆኑባችኋል ፣ እናንተ በምትኖሩባትም አገር ይጣሏችኋል ። ኢያ፡ ፳፫ ፲፫ ፣ መሳ፡ ፪ ፫ ።

(ያልኳችሁን ባታደርጉ ግን) በነሱቸው አደርግ ዘንድ ያሰብኩትን ይህን ጥፋት በናንተ አደርግባችኋለሁ ።

ምዕራፍ ፴፬ ።

እነሆ እናንተ ወደ ከነዓን ትገባላችሁ ፤ ከአውራጃዋ ጋር ለናንተ ርስታችሁ ናት ብለህ ለእስራኤል ልጆች እዘዛቸው ብሎ እግዚአብሔር ለሙሴ ነገረው ። ዘፍ፡ ፲፯ ፰ ።

በምሥራቅ አንጻር ካለች ከኤሌቂም ባሕር ጐን ባለች በኤዶም መገናኛ ጺን የሚባል ዕንጨት ካለበት ምድር ጀምራችሁ በግራ በኩል ያለ ርስት ይሁናችሁ ።

የአዜብም አውራጃዋ ከአቅራቢን ዓቀበት ጀምሮ እስከ ኤናቅ ይደርሳል ፣ በአዜብ በኩል ያለው ፍጻሜውም ቃዴስ በርኔ ነው ፣ ወደ አራድ አገሮችም ይደርሳል ወደ አሴሞናም ይደርሳል (ይወጣል) ። ኢያ፡ ፲፭ ፫ ።

ዳርቻውም በግብጽ ወንዝ (ፈሳሽ) አሴሞና ይዞራል ፣ ወሰኑም ባሕር ነው ። ዘፍ፡ ፲፭ ፲፰ ፣ ኢያ፡ ፬ ፲፭ ።

በምዕራብ በኩል ያለች ድንበራችሁ ታላቂ ባሕር ትሁናችሁ ፣ በምዕራብም በኩል ወሰናችሁ ይህ ነው ።

በመስዕ በኩል ያለም ድንበራችሁ በተራራው አንጻር ካለ ከታላቁ ባሕር ወንዝ ጀምሮ ለናንተ ርስት ይሁናችሁ።

ከተራራው ጀምሮ እስከ ተራራው ድረስ ለናንተ ርስት ይሁናችሁ ፣ እስከ ኤማትም ይደርሳል ፣ መውጫው ፍጻሜውም የሴፋማ ዕጣ የሚሆን አርሴናይን ነው ፣ በመስዕ በኩል ያለ ወሰናችሁም በዚህ ይሁን ።

በምሥራቅ በኩል ያለ ዳርቻችሁም የሴፋማ ዕጣ ከምትሆን ከአርሴናይን ጀምሮ ፣ እስከ አርፌላ ድረስ ይወርዳል።

በምሥራቅም በኩል በከኔሬት ባሕር ጀርባ (አጠገብ) ይገናኛል ። ፪ ነገ፡ ፳፪ ፴ ።

፲ ወይወርድ ደወሉ ኀበ ዮርዳኖስ ወይከውን ሞፃእቱ ባሕረ ኤሌቄ፣ ወዝንቱ ውእቱ ምድርክሙ ምስለ አድዋሊሃ ዘዐውዳ።

ዳርቻውም ወደ ዮርዳኖስ ይወርዳል፣ ፍጻሜውም የኤሌቄ ባሕር ይሆናል፣ በዙርያዋ ካለው ከአውራጃዎቿ ጋር አገራችሁ ይህ ነው፣ አላቸው። ዘኍ ፴፬ ፫።

፲፩ ወነገሮሙ ሙሴ ለደቂቀ እስራኤል ወይቤሎሙ፣ ዛቲ ይእቲ ምድርክሙ እንተ ትወርስዋ ወትትከፈልዋ በከመ አዘዘ እግዚአብሔር ከመ የሀብዎሙ ለተስዐቱ ነገድ ወለመንፈቀ ነገደ ምናሴ።

ሙሴም የምትወርሷትና የምትከፈሏት አገራችሁ ይህ ች ናት ብሎ ለእስራኤል ልጆች ነገራቸው፣ ለምናሴ ነገድ እኩሌታና ለዘጠኙ ነገድ ይሰጧቸው ዘንድ እግዚአብሔር እንዳዘዘው ነገራቸው።

፲፪ እስመ ነሥኡ ነገደ ደቂቀ ሮቤል ወነገደ ደቂቀ ጋድ ወመንፈቀ ነገደ ምናሴ በበአብያተ አበዊሆሙ።

የጋድ ልጆች ነገድና የሮቤል ልጆች ነገድ የምናሴም ነገድ እኩሌታ በየአባቶቻቸው ወገኖች ፈንታቸውን ይዘዋልና። ዘኍ ፴፪ ፪፣ ኢያ ፲፬ ፪።

፲፫ ክልኤቱ ነገድ ወመንፈቀ ነገደ ምናሴ ነሥኡ መክፈልቶሙ ወሠለጡ በማዕዶተ ዮርዳኖስ ዘኀበ ኢያሪኮ እምዘባኑ ዘመንገለ ጽባሕ።

የምናሴ ነገድ እኩሌታና ሁለቱ ነገድ በምሥራቅ በኩል በዮርዳኖስ ማዶ በኢያሪኮ አንጻር በሞዓብ ግራ ፈንታቸውን ጨርሰው ተቀበሉ።

፲፬ ወነበበ እግዚአብሔር ለሙሴ ወይቤሎ፣ ዝንቱ ውእቱ አስማቲሆሙ ለእደው እለ ያስተከፍልዎሙ ይእተ ምድረ አልአዛር ካህን ወያኢሱ ወልደ ነዌ።

እግዚአብሔር ሙሴን እንዲህ ሲል ተናገረው ይህችን አገር የሚያካፍሏቸው ሰዎች ስማቸው ይህ ነው፣ የነዌ ልጅ ኢያሱና ካህኑ አልአዛር ናቸው። ኢያ ፲፬ ፩።

፲፭ ወይነሥኡ አሐደ አሐደ መልአከ እምአሐዱ አሐዱ ነገድ ከመ ያስተከፍልዎሙ ይእተ ምድረ።

ምድሪቱንም ርስት አድርገው ያካፍሉዋቸው ዘንድ ከየነገዱ አንዳንድ አለቃ ይውሰዱ።

፲፮ ወዝንቱ ውእቱ አስማቲሆሙ ለውእቶሙ እደው ዘእምነገደ ይሁዳ ካሌብ ወልደ ዮፎኒ።

የነዚያም ሰዎች ስማቸው ይህ ነው፣ ከይሁዳ ነገድ የተመረጠው የዮፎኒ ልጅ ካሌብ ነው።

፲፯ ወዘእምነገደ ስምዖን ሰላምያል ወልደ ሰሚዩድ።

ከስምዖንም ነገድ የተመረጠው የሰሚዩድ ልጅ ሰላምያል ነው።

፲፰ ወዘእምነገደ ብንያም ኤልዳን ወልደ ሰሰሎን።

ከነገደ ብንያም የተመረጠው የሰሰሎን ልጅ ኤልዳን ነው።

፲፱ ወዘእምነገደ ዳን በቂ ወልደ ዮቅሊ።

ከነገደ ዳን የተመረጠው የዮቅሊ ልጅ በቂ ነው።

፳ ወዘእምነገደ ዮሴፍ ዘእምነገደ ደቂቀ ምናሴ አንሔል ወልደ ሱፋድ።

ከዮሴፍ ልጆች ነገድ ከሚሆን ከምናሴ ልጆች ከነገደ ምናሴም የተመረጠው የሱፋድ ልጅ አንሔል ነው።

፳፩ ወዘእምነገደ ደቂቀ ኤፍሬም ቃሙሔ ወልደ ሰፍጣን።

ከኤፍሬም ልጆች ነገድ የተመረጠው የሰፍጣን ልጅ ቃሙሔ ነው።

፳፪ ወዘእምነገደ ደቂቀ ዛብሎን ኤልሳፍን ወልደ በርናበክ።

ከዛብሎን ልጆች ነገድ የተመረጠው የበርናበክ ልጅ ኤልሳፍን ነው።

፳፫ ወዘእምነገደ ደቂቀ ይሳኮር ፈሊጢሔል ወልደ ሐዛ።

ከይሳኮር ልጆች ነገድ የተመረጠው የሐዛ ልጅ ፈሊጢሔል ነው።

፳፬ ወዘእምነገደ ደቂቀ አሴር አኪሖር ወልደ ሴሌሚ።

ከአሴር ልጆች ነገድ የተመረጠው የሴሌሚ ልጅ አኪሖር ነው።

፳፭ ወዘእምነገደ ደቂቀ ንፍታሌም ፋዳሔል ወልደ ዩምዩድ።

ከንፍታሌም ልጆች ነገድ የተመረጠው የዩምዩድ ልጅ ፋዳሔል ነው።

፳፮ እሉ እሙንቱ ዘአዘዞሙ እግዚአብሔር ከመ ያስፍሩሙ ለደቂቀ እስራኤል ምድረ ከነዓን።

ለእስራኤል ልጆች የከነዓንን ምድር ሰፍረው ያካፍሉዋቸው ዘንድ እግዚአብሔር ያዘዛቸው እሊህ ናቸው።

## ምዕራፍ ፴፭።

፩ ወነበበ እግዚአብሔር ለሙሴ በዐረቢሃ ለሞዓብ ዘኀበ ዮርዳኖስ ዘመንገለ ኢያሪኮ።

በዮርዳኖስ አጠገብ በኢያሪኮ አውራጃ በሞዓብ ግራ እግዚአብሔር ሙሴን እንዲህ ብሎ ተናገረው።

፪ ወይቤሎ አዝዞሙ ለደቂቀ እስራኤል ከመ የሀብዎሙ ለሌዋውያን እምዘይትከፈሉ ርስቶሙ አህጉረ ዘውስቴቶን ይነብሩ ወአድያሚሆን ዘዐውዶን፣ ለውእቶን አህጉር የሀብዎሙ ለሌዋውያን።

ከሚካፈሉት ርስታቸው የሚኖሩባቸውን አገሮች ለሌዋውያን ይሰጡዋቸው ዘንድ የእስራኤልን ልጆች እዘዛቸው የነዚህም አገሮች ዙርያ አውራጃዎች ለሌዋውያን ይስጧቸው። ኢያ ፲፬ ፬፣ ፳፪ ፪፣ ሕዝ ፵፭ ፩።

፫ ወይኩናሆሙ አህጉረ ዘውስቴቶን ይነብሩ ወአዕፃዳቲሆን ይኩናሆሙ ለላሕሞሙ ወለእንስሳሆሙ ።

የሚኖሩባቸው አገሮች ይሁኗቸው፣ የከብቶቻቸውና የላሞቻቸው መሠማሪያ ይሁናቸው ። ዘሌ፣ ፳፭ ፴፬ ።

፬ ወደወሎን ለአህጉር ዘትሁብዎሙ ለሌዋውያን እምሀገሩ ዐሠርተ ምእት በእመት ትሚጥኑ ለአፍአ እምዓውዱ ።

ከአገሩም ለሌዋውያን የምትሰጡዋቸው አገሮች ውስጣቸውን በዙርያ ወደ ውጪ አንድ ሺሕ ክንድ ስፈሩ ።

፭ ዕሥራ ምእት በእመት እምአረፍተ ጽባሐዊ ለሀገር፣ ወዕሥራ ምእት በእመት እምገበሁ መንገለ አዜብ ።

በምሥራቅ በኩል ከአገሩ ቅጽር ጀምራችሁ ሁለት ሺሕ ክንድ በአዜብ በኩል ካለው ከጐኑ ጀምራችሁ ሁለት ሺሕ ክንድ ።

፮ ወዕሥራ ምእት በእመት እምገበሁ ዘመንገለ ባሕር፣ ወዕሥራ ምእት በእመት እምገበሁ ዘመንገለ መስዕ፣ ወሀገሩ ማእከለ ዝንቱ ትኩንክሙ ።

በምዕራብ በኩል ካለው ከጐኑ ጀምራችሁ ሁለት ሺሕ ክንድ በሰሜን በኩል ካለው ከጐኑ ጀምራችሁ ሁለት ሺሕ ክንድ ስፈሩ ከተማውም በመካከል ይሁናችሁ ።

፯ ወሀገር ዘትሁብዎሙ ለሌዋውያን ስሱ አህጉር ለምስካይ ዘትፈልጡ ከመ ይኩናሆሙ ምስካየ ለቀታሊ ወዘእንበለ እላንቱ ዘትሁብዎሙ ባዕዳት አህጉር አርብዓ ወክልኤቱ ።

ለነፍሰ ገዳይ መማፀኛ ይሆኑ ዘንድ ለሌዋውያን ለይታችሁ የምትሰጡዋቸው መማፀኛዎች አገሮች ስድስት ናቸው፣ ከምትሰጡዋቸውም ከነዚህ በቀር አርባ ሁለት አህጉር ስጡዋቸው ። ዘዳ፣ ፬ ፵፩ ፣ ኢያ፣ ፳፩ ፰ ።

፰ ወይከውና ኵሎን አህጉር ዘትሁብዎሙ ለሌዋውያን አርብዐ ወሰማኒተ ወእላንቱሂ አህጉር ምስለ አድያሚሆን ።

ለሌዋውያን የምትሰጡዋቸው አገሮች ሁሉ አርባ ስምንት ይሁኑ፣ እነዚህም አገሮች ከአውራጃዎቻቸው ጋር ናቸው ። ኢያ፣ ፳፩ ፵፩ ።

፱ ወአህጉር ዘትሁብዎሙ እመክፈልቶሙ ለደቂቀ እስራኤል እምዘብዙኅ ብዙኀ፣ ወእምዘውኁድ ውኁደ እምርስቶሙ ዘይትከፈሉ ለለአሐዱ አሐዱ እምኔሆሙ የሀብዎሙ ለሌዋውያን አህጉረ ።

ከእስራኤል ልጆች ዕጣ ለሌዋውያን የምትሰጡዋቸው አገሮች ከብዙው ብዙ፣ ከጥቂቱም ጥቂት ነው፣ ከነሱም ከሚከፈሉት ርስታቸው አንዱም አንዱ ለሌዋውያን አገሮችን ይስጡዋቸው አለው ። ዘኍ፣ ፳፮ ፶፬ ፣ ፴፫ ፶፬ ።

፲ ወነበበ እግዚአብሔር ለሙሴ ወይቤሎ፣ ንግሮሙ ለደቂቀ እስራኤል ወበሎሙ ናሁ ተዐድዉ አንትሙ ዮርዳኖስ ውስተ ምድረ ከነዓን ።

እግዚአብሔር ሙሴን እንዲህ ብሎ ተናገረው፤ እነሆ እናንተ ወደ ከነዓን ለመሄድ ዮርዳኖስን ትሻገራላችሁ ብለህ ለእስራኤል ልጆች ንገራቸው ።

፲፩ ወፍልጡ ለክሙ አህጉረ ምስካይ ከመ ይኩናክሙ ኀበ ይሰኪ ህየ ቀታሊ ኵሉ ዘቀተለ ነፍሰ በኢያእምሮ ።

ባለማወቅ ነፍስን የገደለ ነፍሰ ገዳይ ሁሉ በዚያ ይማጠን ዘንድ መማጠኛ አገሮች ሊሆኑዋችሁ መማጠኛ አገሮችን ለዩ ። ዘፀ፣ ፳፩ ፲፫ ፣ ዘኍ፣ ፴፭ ፲፭ ።

፲፪ ወይኩናክሙ ውእቶን አህጉር ምስካየ እምአበ ደም፣ ከመ ኢይሙት ቀታሊ እስከ ይቀውም ቅድመ ትዕይንት ወይትሐተት ።

እነዚህም አህጉረ ምስካይ ነፍሰ ገዳይ በአደባባይ ቆሞ ነገሩ እስኪመረመር ድረስ ነፍስ የገደለ ሰው እንዳይሞት ከባለ ደሙ ይጠበቅበት ዘንድ ሀገረ ምስካይ ይሁኗችሁ ።

፲፫ ወውእቶን አህጉር እለ ትሁቡ ስሱ አህጉረ ምስካይ ይኩናክሙ ።

እነዚያም የምትሰጡዋቸው ስድስት አገሮች አህጉረ ምስካይ (መማጠኛ) ይሁኗችሁ ። ዘኍ፣ ፴፭ ፮ ።

፲፬ ሠላሰ አህጉረ ትፈልጡ በማዕዶተ ዮርዳኖስ፣ ወሠላሰ አህጉረ ትፈልጡ በምድረ ከነዓን ።

ለእስራኤል ልጆች መማጠኛ ይሆኗቸው ዘንድ በዮርዳኖስ ማዶ ሦስት አገሮችን በከነዓንም ሦስት አገሮችን ለዩ ።

፲፭ ወምስካየ ይኩናሆሙ ለደቂቀ እስራኤል፣ ለግዩራኒ ወለፈላሲኒ ዘሀለዉ ኀቤክሙ ይኩናሆሙ ምስካየ እላንቱ አህጉር ከመ ይስኪ ህየ ኵሉ ዘቀተለ ነፍሰ በኢያእምሮ ።

እነዚያም አገሮች ሳያውቅ ነፍስ የገደለ ሁሉ በነዚያ ይማጠን ዘንድ በናንተ ዘንድ ለሚኖሩ ስደተኛና መጻተኛ መማጠኛ ይሁኗቸው ። ዘኍ፣ ፴፭ ፲፮ ።

፲፮ ወእመሰ በንዋየ ሐጺን ዘበጦ፣ ወሞተ ቀታሊ ውእቱ ሞተ ለይሙት ዘቀተለ ።

በጦር ወግቶት ቢሞት ግን ያ ሰው ነፍሰ ገዳይ ነውና ያ የገደለ ሰው ይሙት ። ዘፀ፣ ፳፩ ፲፪ - ፲፬ ።

፲፯ ወለእመኒ በእብን ወገሮ አው አውደቀ ላዕሌሁ እምእዴሁ ወሞተ፣ ቀታሊ ውእቱ ሞተ ለይሙት ዘቀተለ ።

በደንጊያ መትቶ ቢገድለው ወይም በእጁ ወርውሮ ቢገድለው ያ ሰው ነፍሰ ገዳይ ነውና፣ ያ የገደለ ሰው ይሙት ። ዘኍ፣ ፴፭ ፳፩ ፣ ዘዳ፣ ፲፱ ፲፪ ።

፲፰ ወለእመኒ በንዋየ ዕፅ ዘበጦ አው አውደቀ ላዕሌሁ እምእዴሁ ወሞተ፣ ቀታሊ ውእቱ ሞተ ለይሙት ዘቀተለ ወአበ ደም ለሊሁ ይቅትሎ ።

በዕንጨትም (በመንዶ) መትቶ ቢገድለው ወይም ትልቅ ግንድ ገፍቶ ጥሎበት ቢሞት ነፍሰ ገዳይ ነውና ያ የገደለው ሰው ይሙት፣ ባለ ደምም (አስፈርዶ) ይግደለው ።

፲፱ ወለእመኒ ጽልአ ይጸልእ ወአውደቀ ላዕሌሁ ዘከነ ንዋየ እንዘ ይጸንሖ ወሞተ፣ ቀታሊ ውእቱ ሞተ ለይሙት ዘቀተለ፣ ወአበ ደም ለይቅትሎ በኀበ ረከቦ ።

ጠብንም ቢጣላው ሸምቆም ቢሆን በማናቸውም መሣሪያ መትቶ ቢሞት ነፍሰ ገዳይ ነውና፣ ያ የገደለው ሰው ይሙት፣ ባለ ደሙም በገኘበት በታ ይግደለው፣ (ከስፈረደ በኋላ ነው) ። ኢያ፣ ፳፫ ፮ ።

፳፪ ወእመሰ ግብተ ውእቱ እንዘ ኢይጸልኦ ወአውደቀ ላዕሌሁ ዘከነ ንዋየ እንዘ ኢይጸንሖ ፡ አው በዘከነ እብን ወሞተ ቦቱ ወቀተሎ እንዘ ኢየአምሮ ወኢከነ ጸላኢሁ ወኢይፈቅድ ያሕስም ላዕሌሁ ፡ ይሕትቱ ትዕይንት ማእከለ ቀታሊ ወማእከለ አበ ደም በከመ ዝንቱ ፍትሕ ።

፳፭ ወያድኅንዎ ትዕይንት ለዘቀተለ እምእበ ደም ወይወስድዎ ትዕይንት ውስተ ሀገረ ምስካይ ኀበ ይስኪ ወይነብር ህየ እስከ ይመውት ካህን ዐቢይ ዘቀብዕዎ ቅብዐ ቅድሳት ።

፳፮ ወለእመሰ ወፅአ አፍአ ቀታሊ ውስተ አድዋለ ሀገር እንተ ውስቴታ ሰከየ ህየ ወረከቦ አበ ደም ለቀታሊ በአፍአ ውስተ አድዋለ ሀገር ዘምስካይ ፡ ወቀተሎ አበ ደም ለቀታሊ አልቦ ጌጋይ ።

፳፯ እስመ ውስተ ሀገረ ምስካይ ይነብር እስከ ይመውት ካህን ዐቢይ ፡ ወእምድኅረ ሞተ ካህን ዐቢይ ይገብእ ውስተ ምድረ ብሔሩ ።

፳፱ ወከመዝ ይኩንክሙ ፍትሐ ኵነኔ በመዋዕሊክሙ በኵሉ በሐውርቲክሙ ።

፴ ኵሉ ዘቀተለ ነፍሰ ወዘለፎ ማሕተት ትቀትልዎ ለቀታሊ ፡ ወስምዕ አሐዱ ኢይከውን ማሕተት ለአቅትሎ ነፍስ ።

፴፩ ወኢትንሥኡ ቤዛ በእንተ ነፍስ እምቀታሊ ዘጌጋዩ ለመዊት ሞተ ለይሙት ።

፴፪ ወኢትንሥኡ ቤዛ ከመ ትጕይይዎ ውስተ ሀገረ ምስካይ ከመ ይንበር ከዕበ ውስተ ምድር እስከ ይመውት ካህን ዐቢይ ።

፴፫ ወኢትግበርዋ ቀታሊተ ለምድር እንተ ውስቴታ ትነብሩ ፡ እስመ ውእቱ ደም ዘይፈልስ ቀታሊተ ለምድር ወኢትሠረ ሎቱ ምድር ለዘከዐወ ደመ ላዕሌሃ ።

፴፬ ወኢታገምኗዋ ለምድር እንተ ውስቴታ ትነብሩ አንትሙ ፡ ወእንተ ውስቴታ አነ አኀድር ምስሌክሙ ፡ እስመ አነ ውእቱ እግዚአብሔር ዘአኀድር ማእከሎሙ ለደቂቀ እስራኤል ።

ምዕራፍ ፴፮ ።

፩ ወመጽኡ መላእክተ ነገደ ቤተ አበዊሆሙ ለገለዓድ ወልደ ማኪር ወልደ ምናሴ ዘእምነገደ ደቂቀ ዮሴፍ ወቆሙ ቅድመ ሙሴ ወቅድመ አልአዛር ካህን ወቅድመ መላእክተ አብያተ አበዊሆሙ ለደቂቀ እስራኤል ።

፪ ወይቤሉ አዘዘ እግዚአብሔር ለእግዚእነ ከመ የሀቦሙ ምድረ ርስቶሙ በበመክፈልቶሙ ለደቂቀ እስራኤል ወአዘዘ እግዚአብሔር ለእግዚእነ ከመ የሀቦን መክፈልተ ሰለጳአድ እኁነ ለአዋልዲሁ ።

፫ ወይከውና እንስትያሆሙ ለአሐዱ እምነገዶሙ ለደቂቀ እስራኤል ወይወጽእ መክፈልቶን እመክፈልተ አበውሆን ወይትዌሰክ ውስተ ካልእ መክፈልተ ነገድ ኀበ አውሰብ ፡ ወይወፅእ እመክፈልተ ርስትነ ።

፳፪ ሳይጣላው ድንገት መትቶት ቢሞት ሳይሸምቅም ለሞት የሚያበቃ መሣሪያ ቢጥልበት ወይም በተገኘው ድንጊያ መትቶት ቢሞትበት ሳያውቅና ጠላቱም ሳይሆን ቢገድለው በርሱም ክፉ ነገር ለማድረግ ሳይወድ ቢገድለው ፡ ሠራዊቱ እንደዚህ ፍርድ በባለ ደሙና በገዳዩ መከከል ይመርምሩ ። ዘኍ፡ ፴፭ ፲፪ ።

፳፭ ሠራዊቱም ነፍሰ ገዳዩን ከባለ ደሙ ያድኑት ፡ ሠራዊቱ ወደሚማጠንበት ወደ ሀገረ ምስካይ ይውሰዱት ፡ ቅብዓ ክህነት የቀቡት ታላቁ ካህን እስኪሞትም ድረስ በዚያ ይኑር ። ዘሌ፡ ፳፩ ፲ ፡ ኢያ፡ ፳ ፯ ።

፳፮ ነፍሰ ገዳዩ ከዚያ ከተማጠነበት አገር ዳርቻ ወጥቶ ቢሄድ ግን ባለ ደሙም ከተማጠነበት አገር አውራጃ ወጥቶ በአፍኣ አግኝቶ ያነን ነፍሰ ገዳይ ባለ ደሙ ቢገድለው ዕዳ የለበትም ።

፳፯ ታላቁ ካህን (ሊቀ ካህናቱ) እስኪሞት ድረስ በአገረ ምስካዩ ይኖራልና ሊቀ ካህናቱ ከሞተ በኋላ ግን ወደ አገሩ ይመለሳል ። ዘፀ፡ ፳፪ ፪ ።

፳፱ በዘመናችሁ በአገራችሁ ሁሉ ይህ የቀጣት ፍርድ እንደዚህ ይሁናችሁ ። ዘኍ፡ ፳፯ ፲፩ ።

፴ ነፍስ የገደለ ሰው ሁሉ ምስክር ቢመሰክርበት ገዳዩን ግደሉት ፡ አንድ ምስክር ግን ነፍስን ለማስገደል ምስክር አይሁን ። ዘዳ፡ ፲፯ ፯ ፡ ፲፱ ፲፯ ፡ ማቴ፡ ፲፰ ፲፯ ።

፴፩ ፍርዱ በደሉ ለሞት ከሚያበቃው ከነፍሰ ገዳዩ ማማለጃን አትቀበሉ ፡ ለሞት የሚያበቃው ቢሆን ይሙት ።

፴፪ ሊቀ ካህናቱ እስኪሞት ድረስ በሌላ ሀገረ ምስካይ ለመኖር ወደ ሌላ ሀገረ ምስካይ ቃሸሹት ዘንድ ማማለጃን አትቀበሉ ።

፴፫ ምድርን ነፍሰ ገዳይ የሚያደርጋት ያ ደም ነውና በላይዋ ላይ ደም ያፈሰሰውንም ሰው ይቅር አትበሉምና የምትኖሩበት አገራችሁን ነፍሰ ገዳይ አታድርጓት ።

፴፬ በእስራኤል ልጆች መከከል በረድኤት የምኖር እኔ እግዚአብሔር ነኝና እናንተ የምትኖሩበት እኔም ከናንተ ጋራ የምኖርበትን ምድር አታሳድፉዋት ።

ምዕራፍ ፴፮ ።

፩ ከዮሴፍ ልጆች ነገድ የተወለደ የምናሴ ልጅ የማኪር ልጅ የገለዓድ የአባቶቹ ወገን ነገድ አለቆች መጥተው በካህኑ በአልአዛርና በሙሴ ፊት በእስራኤል ልጆች አባቶች ወገኖች አለቆችም ፊት ቆሙ ። ዘኍ፡ ፳፮ ፳፱ ።

፪ ለእስራኤል ልጆች በየፈንታቸው ርስታቸው የሚሆን አገርን ትሰጣቸው ዘንድ አንተን ጌታችንን እግዚአብሔር አዘዘህ ፡ የወንድማችን የሰለጰአድንም ፈንታ ለሴቶች ልጆቹ ትሰጣቸው ዘንድ አንተን ጌታችንን እግዚአብሔር አዘዘህ ። ዘኍ፡ ፳፯ ፶፭ ፡ ኢያ፡ ፲፯ ፬ ።

፫ ከእስራኤል ነገድ ላንዱም ላንዱም ሚስቶች ይሆናሉ ፈንታቸውም ከአባታቸው ፈንታ ወጥቶ ወደ ገቡበት ወደ ሌላ ነገድ ፈንታ ይጨመራል ከርስታችንም ፈንታ ይወጣል ። ዘኍ፡ ፳፯ ፬ ።

| | | |
|---|---|---|
| ወለእመ ይከውን ይወፅእ እምደቂቀ እስራኤል ወይገብእ ርስቶሙ ውስተ ርስተ ካልእ ነገድ ኀበ አውሰበ እስመ ናሁ ይወፅእ እምውስተ ርስቶሙ ወመክፈልቶሙ ለነገደ አበዊነ ። | ፬ | ከእስራኤል ልጆች ወዋቶ ርስታቸው ወደ ገቡበት ወደ ሌላ ነገድ ርስት የሚገባ ከሆነ፣ እነሆ ከአባቶቻችን ነገድ ፈንታና ርስት ይወጣልና ስጡን አሉ ። |
| ወአዘዞሙ ሙሴ ለደቂቀ እስራኤል በትእዛዘ እግዚአብሔር ወይቤሎሙ ከመዝ ለነገደ ደቂቀ ዮሴፍ ። | ፭ | ሙሴም በእግዚአብሔር ትእዛዝ የእስራኤልን ልጆች አዘዛቸው፣ የዮሴፍን ልጆች ነገድንም እንዲህ አላቸው ። |
| ዝንቱ ውእቱ ቃል ዘአዘዘን እግዚአብሔር ለአዋልደ ሰለጰአድ ወይቤ ዘአደሞን በቅድሜሆን ለያውስባ ወዳእሙ እምደቂቀ አበዊሆን ለያውስባ ። | ፮ | እግዚአብሔር የሰለጰአድን ልጆች ያዘዛቸው ቃል ይህ ነው፣ በፈቃዳቸው የወደዱትን ያግቡ፣ ነገር ግን ከአባቶቻቸው ልጆች ያግቡ ። ዘኍ፡ ፴፮ ፫ ፲ ። |
| ወኢይግባእ ርስቶሙ ለደቂቀ እስራኤል እምነገድ ለነገድ እስመ አሐዱ አሐዱ እምኔሆሙ ውስተ ርስተ አበዊሆሙ ይትልዉ ደቂቀ እስራኤል ። | ፯ | የእስራኤል ልጆች እያንዳንዳቸው ፈንታቸውን ይከተሉ እንጂ ርስት ከነገዱ ነገድ ወደ ሌላ ነገድ አይግባ አለ። |
| ወኵላ ወለት እንተ ተኀሥሥ ርስተ እምደቂቀ እስራኤል አሐደ እምነገዳ ለታውስብ፣ ከመ ይኅሥሡ ደቂቀ እስራኤል አሐዱ አሐዱ ርስተ ለርእሱ ወርስተ አቡሁ ። | ፰ | የእስራኤል ልጆች ከነሳቸው አንዱም አንዱም ርስቱን ያብቁንም ርስት ይፈልጉ ዘንድ ከእስራኤል ልጆች ርስት የምትፈልግ ሴት ልጅ ሁሉ ከነገዷ አንድ ሰው ታግባ። |
| ወኢይግባእ ርስት እምነገድ ውስተ ካልእ ነገድ፣ አላ አሐዱ አሐዱ ውስተ መክፈልቶሙ ይትልዉ ደቂቀ እስራኤል ። | ፱ | የእስራኤል ልጆች አንዱም አንዱም ፈንታቸውን ይከተሉ እንጂ ርስት ከነገድ ወደ ሌላ ነገድ አይግባ ። |
| ወገብራ አዋልደ ሰለጰአድ መሐላ፣ ወቴርሳ፣ ወሔግላ፣ ወሚልካ፣ ወኑኃ፣ በከመ አዘዘ እግዚአብሔር ለሙሴ ። | ፲ | የሰለጰአድ ልጆች ቴርሳና መሐላ፣ ሚልካና ሔግላ፣ ኑሐም እግዚአብሔር ሙሴን እንዳዘዘው አደረጉ ። |
| ወአውሰባ ዘእምደቂቀ ቅሩባን ዘእምነገደ ደቂቀ ምናሴ ወልደ ዮሴፍ ወገብአ መክፈልቶን ውስተ ነገደ ሕዝበ አበዊሆን ። | ፲፩ | አቅራቢያቸው ከሚሆኑ ልጆች ከዮሴፍ ልጅ ከምናሴ ልጆች አገቡ፣ ፈንታቸውንም ወደ አባቶቻቸው ወገኖች ነገድ ተመለሰ። ዘኍ፡ ፳፮ ፩ ። |
| ዝንቱ ውእቱ ትእዛዝ ወኵነኔ ወፍትሕ ዘአዘዘ እግዚአብሔር በእደ ሙሴ፣ በዐረቢሆ ለሞዓብ ዘኀበ ዮርዳኖስ ዘመንገለ ኢያሪኮ ። | ፲፪ | በዮርዳኖስ ማዶ በኢያሪኮ አንጻር ባሉቹ በሞዓብ ግራ እግዚአብሔር በሙሴ ቃል ያዘዘው ትእዛዝ (ዘጠኙ ሕግጋት) ፍርድ ፍትሕ አምስት መቶ ሰባ "ወነበበ„ ይህ ነው። |

ኦሪት ዘኍልቍ ተፈጸመ፡
ወስብሐት ለእግዚአብሔር ዘፈጠረ ኵሎ ዓለመ
አሜን ።

የእስራኤልን ቍጥር የሚናገር መጽሐፍ ደረሰ ተፈጸመ፣
ለእግዚአብሔር የዘለዓለም ክብርና ምስጋና ይግባው፣
አሜን።

# ኦሪት ዘዳግም

ምዕራፍ ፩ ።

፩ ዝንቱ ውእቱ ነገር ዘነገሮሙ ሙሴ ለኵሉ እስራኤል በማዕ
ዶተ ዮርዳኖስ በመንገለ ዐረቢያ በኀበ ባሕረ ኤርትራ በማ
እከለ ፋራን ወጦፌል ወለባን ወአውሎን ወዘኬረብ ።
፪ በዐሡር መዋዕል እምኮሬብ በፍኖተ ደብረ ሴይር እስ
ከ ቃዴስ በርኔ ።

፫ ወኮነ አመ አርብዓ ዓም አመ ዓሡር ወአሚሩ ወርኅ
አመ ሠርቀ ወርኅ ነገሮሙ ሙሴ ለኵሉ ደቂቀ እስራኤል
ኵሎ ዘአዘዞ እግዚአብሔር ይንግሮሙ ።

፬ እምድኅረ ቀተሎ ለሴዎን ንጉሠ አሞሬዎን ዘይነብር
ውስተ ሐሴቦን ወለዖግ ንጉሠ ባሳን ዘይነብር ውስተ አስ
ጣሮት ወኤንድራይን ።

፭ በማዕዶተ ዮርዳኖስ ውስተ ምድረ ሞአብ ወአኀዘ ሙሴ
ይንግር ዘንተ ሕገ ወይቤ እግዚአብሔር አምላክነ ነገረነ
በኮሬብ ወይቤለነ አክለክሙ ኀዲሮት ውስተ ዝንቱ ደብር፡
፯ ተንሥኡ እንከ ወሑሩ ወባኡ ውስተ ደብረ አሞሬዎን
ወውስተ ኵሉ ማኅደረ ዓረብ ውስተ ደብሩ ወውስተ ገዳ
ሙ ወውስተ ሊብ ወውስተ ጳራሊያ ዘምድረ ከነአን ወአን
ጢሊባኖን እስከ ፈለግ ዐቢይ ፈለገ ኤፍራጥስ ።

፰ ናሁ ወሀብኩክሙ ይእተ ምድረ እንተ መሐልኩ ለአ
በዊክሙ ቅድሜክሙ ለአብርሃም ወለይስሐቅ ወለያዕቆብ
ከመ እሁቦሙ ሎሙ ወለዘርኦሙ እምድኅሬሆሙ ምድረ
እንተ ትውኅዝ ሐሊበ ወመዓረ ።
፱ ወእቤለክሙ በውእቱ መዋዕል እንዘ እብል ኢይክል
ባሕቲትየ ፀዊሮተክሙ ፤ እስመ አብዝኀነ እግዚአብሔር
አምላክነ ።
ወናሁ ብዙኃን አንትሙ ዮም ከመ ከዋክብተ ሰማይ።
፲ ወያብዝኃክሙ እግዚአብሔር አምላክሙ ለአበዊነ
ምእልፊተ ወይባርክሙ በከመ ይቤለክሙ ።
፲፩ ወእፎ እክል ባሕቲትየ ፆማክሙ ወሥራሕክሙ ወተ
በሀሎተክሙ ።
፲፪ አምጽኡ ለክሙ አደወ ጠቢባነ ወለባውያነ ወም ፖ
ራነ እምነገድክሙ ወእሠይሞሙ ለክሙ መስፍንተ ሎ ።

ምዕራፍ ፩ ።

በዘኬሬብያና በአውሎን በሉብንና በጦፌል ፤ በፋራን
መከከል በኤርትራ ባሕር ዘንድ በግራዋ በኵል በዮርዳኖስ
ማዶ ለእስራኤል ሁሉ ሙሴ የነገራቸው ይህ ነው ።
ከኮሬብ ጀምሮ እስከ ቃዴስ በርኔ ድረስ በሴይር ተራ
ራ መንገድ በዓሥር ቀን ተጕዘው በአሥረኛው ቀን ያስተ
ማረው ትምህርት ይህ ነው ። ዘዳ፤ ፪ ፲፬ ፤ ፱ ፳፫ ።
ከግብጽ በወጡ በአርባው ዘመን በአሥራ አንደኛው
ወር (በየካቲት መባቻ) ለእስራኤል ልጆች ሁሉ እንዲነግራ
ቸው እግዚአብሔር ያዘዘውን ሁሉ ለእስራኤል ልጆች
ሁሉ ነገራቸው ። ዘኍ፤ ፲፭ ፴፭ ፤ ፩ ሳሙ፤ ፳፩ ፩ ።
በኤንድራይንና በአስጣሮት የሚኖር የባሳን ንጉሥ
ዖግን በሐሴቦን የሚኖር የአሞሬዎንን ንጉሥ ሴዎንን በሞ
ዓብ አውራጃ በዮርዳኖስ ማዶ ከገደሉት በኋላ የነገራቸው
ነገር ይህ ነው ። ዘኍ፤ ፳፩ ፴፫ ፤ ኢያ፤ ፲፪ ፬ ።
ሙሴ ይህን ሕግ ያስተምር ጀመረ፤ ፈጣሪያችን እግዚ
አብሔር በዚህ ተራራ መስፈር በቃችሁ ብሎ ሙሴ በኮ
ሬብ ነገረን አለ ። ዘኍ፤ ፲ ፲፩ ፤ ዘዳ፤ ፪ ፫ ።
እንግዲህ ከዚህ ተነሥታችሁ ወደ አሞሬዎን ተራራ
ወደ ዓረብም አገር ሁሉ ወደ ደጋውም ወደ ቈላውም
ወደ ቀኙም ወደ ግራውም እስከ ታላቁ ኤፍራጥስ ወንዝ
ድረስ በከነዓን አገር ወደ ደሴቱም ወደ ደጋውም ተነ
ሥታችሁ ግቡ ። ዘፍ፤ ፲፪ ፯ ፤ ፲፭ - ፲፰ ።
ለነሳቸውና ከነሳቸውም በኋላ ለልጆቻቸው እሰጣቸው
ዘንድ ለአባቶቻቸው ለአብርሃም ለይስሐቅና ለያዕቆብ የማ
ልሁላቸውን በፊታችሁ የምታዩዋትን ማርና ወተት የም
ታፈስውን ያችን አገር እነሆ ሰጥቻችኋለሁ ።
ፈጣሪያችን እግዚአብሔር አብዝቶናልና ብቻዬን መሥ
ራት (መፍረድ) አልችልም ብዬ በዚያ ወራት ነገርኋችሁ።

እነሆ እናንተ እንደ ሰማይ ከዋክብ ዛሬ ብዙዎች ናችሁ፤
ያባቶቻችን ፈጣሪ እግዚአብሔር አበዛችኋለሁ ብሎ
እንደ ተናገረ የብዙ ብዙ አድርጎ ያብዛችሁ ይባርካችሁ።
ድካማችሁን ክርክራችሁንና ሸክማችሁን ብቻዬን
እንደምን እችላለሁ ፤ ። ፩ ነገ፤ ፫ ፰ ፤ ፪ ቆሮ፤ ፲፩ ፳፰ ።
ለናንተ ሹማምንት አድርጌ እሾማቸው ዘንድ ከየነገ
ዶቻችሁ አዋቆችን አስተዋዮችን ጥበበኞችን ሰዎች መርጣ
ችሁ አምጡ ። ዘፀ፤ ፲፰ ፳፩ ፤ ዘኍ፤ ፲፩ ፲፯ ።

፲፫ ወአውሥእክሙኒ ወትቤሉኒ ሠናይ ዝንቱ ቃል ወትቤሉኒ ግበር ከማሁ ።

ይህ ቃል ያማረ የተወደደ ነው ፡ አሁን እንደ ተናገርከው አድርግ ብላችሁ መለሳችሁልኝን ፤ ።

፲፬ ወነሣእኩ እምውስቴትክሙ እደወ ጠቢባነ ወማእምራነ ወለባውያነ ወሤምክዎሙ ላዕሌክሙ ይኩኑክሙ መላእክተ ዓሠርቱ ምእት ወመላእክተ ምእት ፡ ወመላእክተ ሐምሳ ፡ ወመላእክተ ዐሠርቱ ፡ ወጸሐፍቶሙ ለመኳንንቲክሙ ።

እኔም ከናንተ ውስጥ አዋቆችን ብልሆችን አስተዋዮችን መርጬ የሺ አለቆች ፡ የመቶ አለቆች ፡ የአምሳ አለቆች ፡ የዓሥር አለቆች አድርጌ ሾምሁላችሁ ለመኳንንቶቻችሁም ጸሐፍቶች አደርግኋቸው ።

፲፭ ወእቤሎሙ በውእቱ መዋዕል ስምዑ ማእከለ አኀዊክሙ ወማእከለ ግዩር ፡ ወማእከለ ብእሲ ወእኁሁ ፡ ወአግብኡ ፍትሐ በጽድቅ ።

ወንድም ከወንድሙ ጋር በተጣላ ጊዜ ነገሩን ሰምታችሁ በመጻተኛውና በወንድሞቻችሁ መካከል እውነት ፍረዱ ብዬ በዚያ ወራት ነገርኋቸው ። ዮሐ፡ ፯ ፳፬ ።

፲፮ ወኢትንሥኡ ገጸ በፍትሕ ፡ ኢ ለንኡስ ወኢ ለዐቢይ ወኩንኑ በጽድቅ ወኢትንሥኡ ገጸ ሰብእ እስመ ፍትሕ ዘእግዚአብሔር ውእቱ ፡ ወለእመቦ ዘዐፀበክሙ ነገር ታየበርዎ ኀቤየ ወእሰምዖ ።

በፍርድ ጊዜ ለትንሹም ለትልቁም ፊት አይታችሁ አታድሉ ፡ እውነተኛው ፍርድ የእግዚአብሔር ግንዘብ ነውና የሰው ፊት አይታችሁ አታድሉ ፡ የረቀቃችሁም ፍርድ ቢኖር ወደኔ አድርሱት ፡ እኔ እሰማዋለሁ ።

፲፯ ወአዘዝኩክሙ በውእቱ መዋዕል ኵሎ ቃለ ዘትገብሩ ።

የምትሠሩትን ሥራ ሁሉ በዚያ ወራት አዘዝኋችሁ ።

፲፰ ወግዕዝነ እምኮሬብ ወሖርነ ኵሎ ገዳመ ዐቢየ ወግሩመ ዘርኢክሙ በፍኖተ ደብረ አሞሬዎን በከመ አዘዘነ እግዚአብሔር አምላክነ ወበጻሕነ እስከ ቃዴስ በርኔ ።

ፈጣሪያችን እግዚአብሔር እንዳዘዘን ከኮሬብ ተጕዘን በአሞሬዎን ተራራ መንገድ ያያችሁት ይህን የሚያስፈራ ታላቅ ተራራ ምድረ በዳ ተጕዘን እስከ ቃዴስ በርኔ ደረስን።

፲፱ ወነገርኩክሙ በውእቱ መዋዕል ወእቤለክሙ ብጽሑ እስከ ደብረ አሞሬዎን ዘይሁበክሙ እግዚአብሔር አምላክክሙ ።

ፈጣሪያችሁ እግዚአብሔር እስከ ሚሰጣችሁ እስከ አሞሬዎን ተራራ ድረስ ሂዱ ብዬ በዚያ ወራት ነገርኋችሁ ። ፩ ሳሙ፡ ፲፯ ፯፡ ፳፱ - ፴፫፡ ዘዳ፡ ፰ ፲፬ ።

፳ ወናሁ ርእዩ ከመ ወሀበክሙ እግዚአብሔር አምላክክሙ ይእተ ምድረ ቅድመ ገጽክሙ ዕርጉ እንከ ወተዋረስዋ በከመ ይቤሎሙ እግዚአብሔር አምላክሙ ለአበዊነ ኢትፍርሁ ወኢትደንግፁ ።

እነሆም ፈጣሪያችሁ እግዚአብሔር ያችን ምድር በፊታችሁ እንደ ሰጣችሁ እዩ (አስተውሉ) ያባቶቻችን ፈጣሪ እግዚአብሔር ትወርሷታላችሁ እንዳላቸው እንግዲህ ውረሷት አትፍሩ አትደንግጡ ። ዘዳ፡ ፴፩ ፰፡ ኢያ፡ ፩ ፱ ።

፳፩ ወእምዝ መጻእክሙ ኵልክሙ ኀቤየ ወትቤሉኒ ንፈኑ እደወ ቅድሜነ ይርአይዋ ለይእቲ ምድር ለነ ፡ ወይዜንዉነ ዜናሃ ለይእቲ ፍኖት እንተ ሀለወነ ንዕርግ ውስቴታ ፡ ወለአህጉርኒ እለ ሀለወነ ንበእ ውስቴቶን ።

ከዚህ በኋላ ሁላችሁ ወደኔ መጥታችሁ ከኛ አስቀድሞ ሰዎችን ልከን ያችን አገር ይዩልን ፡ ወደነሳቸው እንገባ ዘንድ ያለን እነዚያን አገሮችና ወደዚ እንወጣ ዘንድ ያለን የዚያች አገር ጐዳናንና ወሬዋን ይንገሩን አላችሁኝ ።

፳፪ ወአደመኒ ውእቱ ነገር ወነሣእኩ እምውስቴትክሙ ዐሠርተ ወክልኤተ እደወ በበአሐዱ ብእሲ እምነገድ ።

ያም ነገር ደስ አሰኘኝ ከየነገዱ አንዳንድ ሰው መርጬ ከናንተ ዓሥራ ሁለት ሰዎች ተቀበልኩ ። ዘኁ፡ ፲፫ ፫ ።

፳፫ ወሖሩ ወዐርጉ ውስተ ደብር ወበጽሑ ውስተ ቈላተ ዐጽቅ ወርእይዋ ።

ሄደውም ወደ ተራራው አገር ወጥተው የወይን ዘለላ ወዳለበት ቈላ ደርሰው ያችን አገር አዩዋት ።

፳፬ ወነሥኡ ምስሌሆሙ እምፍሬሃ ለይእቲ ምድር ወአምጽኡ ኀቤነ ወንቤ ሠናይት ምድር ዘይሁበነ እግዚአብሔር አምላክነ ።

ከዚያች አገር ምድር ፍሬ ይዘው ወደኛ አመጡልን እኛም ፈጣሪያችን እግዚአብሔር የሚሰጠን ያችን አገር መልካም ናት አልን ። ዘኁ፡ ፲፫ ፳፪፡ ዘዳ፡ ፱ ፲፫ ።

፳፭ ወአበይክሙ ዐሪገ ወክሕድክሙ ቃለ እግዚአብሔር አምላክክሙ ።

ወደዚ መውጣትን እምቢ አላችሁ ፡ የፈጣሪያችሁ የእግዚአብሔርን ቃል ከዳችሁ ። ዘዳ፡ ፩ ፴፫ ፡ ኢያ፡ ፩ ፲፰ ።

፳፮ ወአንጐርጐርክሙ በውስተ ተዓይኒክሙ ፡ ወትቤሉ እስመ ይጸልአነ እግዚአብሔር አውጽአነ እምድረ ግብጽ ከመ ያግብአነ ውስተ እዴሆሙ ለአሞሬዎን ወከመ ይሥርወነ ፡ አይቴ እንከ ነዐርግ ንሕነ ።

በሰፈራችሁም አንጐራጐራችሁ እግዚአብሔር ጠልቶናልና በአሞሬዎን እጅ ሊጥለን ከግብጽ ምድር አወጣን ፡ እንግዲህ እኛ ወዴት እንወጣለን ፤ አላችሁ ።

፳፯ ወባሕቱ አኀዊክሙ አክሐድዎ ለልብክሙ ወይቤሉክሙ ዐቢይ ሕዝብ ወብዙኅ ወይጸንዑ እምኔክሙ ፡ ወአህጉሪሆሙኒ ዐበይት ወበቶን ጥቅም ዘይበጽሕ እስከ ሰማይ ወርኢነ በህየ ደቂቀ ለእለ ያርብኅ ።

ነገር ግን ወንድሞቻችሁ (ሕዝቡ) ወገኑ ፈጽሞ ብዙ ነው ፡ ከናንተ ይበረታል ፡ አምባዎቻቸውም የፀኑ ናቸው እስከ ሰማይ የሚደርስ ቅጽር አላቸው በዚያ የአርበኞችን ልጆች አየን ብለው ልቡናችሁን አስከዱት ።

ወእቤለክሙ ኢትፍርሁ ወኢትደንግፁ እምኔሆሙ ።

እኔም ከነሱ የተነሳ ያጠፉናል ብላችሁ አትፍሩ ።

፳፰ እግዚአብሔር አምላክክሙ ውእቱ ይፀብእ ለክሙ ምስሌክሙ ወውእቱ የሐውር ቅድመ ገጽክሙ በከመ ኵሉ ዘገብረ ለክሙ በምድረ ግብጽ ።

ፈጣሪያችሁ እግዚአብሔር ከናንተ ጋር ሆኖ ይዋጋላችኋል ፡ በግብጽ አገር እንዳደረገላችሁ ሁሉ በፊታችሁ የሚሄድ እርሱ ነው ። ዘፀ፡ ፲፬ ፲፬ ፡ ነህ፡ ፬ ፳ ።

| | | |
|---|---|---|
| ወበውስተ ገዳም ዘርኢክሙ በከመ ሴሰየክሙ እግዚአብሔር አምላክክሙ ዘከመ ይሴሲ ብእሲ ውሉዶ በኵሉ ፍኖት እንተ ሖርክሙ እስከ በጻሕክሙ ውስተ ዝንቱ መካን ። | ፴፩ | አባት ልጁን እንዲመግብ በዚህ በያችሁት ምድረ በዳም ወደዚህ ቦታ እስክትደርሱ ድረስ በሄዳችሁበት ጐዳናም ሁሉ ፈጣሪያችሁ እግዚአብሔር እንደ መገባችሁ መጠን። |
| ወኢአመንክሙሁ በዝንቱ ቃል ለእግዚአብሔር አምላክክሙ ዘየሐውር ቅድሜክሙ ውስተ ፍኖት ከመ ይኅረይ ለክሙ መካነ ወይምርሐክሙ ሌሊተ በእሳት ከመ ያርኢክሙ ፍኖተ ዘተሐውሩ በቲ መዓልተኒ በደመና ። | ፴፪ | በቦታን ይመርጥላችሁ ዘንድ ሌሊት በዓምደ እሳት፥ ቀንም በደመና የምትሄዱበትን ጐዳና ያሳያችሁ ዘንድ በጐዳናው ፊታውራሪ ሆኖ የሚሄድ ፈጣሪያችሁ እግዚአብሔርን በዚህ ቃል አላመናችሁትም ። ዘፀ፡ ፲፫ ፳፩ ። |
| ወሰምዐ እግዚአብሔር ቃለ ነገርክሙ ወተምዐ ወመሐለ ወይቤ ከመ ኢይሬእይዋ እሉ እደው ለይእቲ ምድር ቡርክት ዘመሐልኩ ለአበዊሆሙ ዘእንበለ ካሌብ ወልደ ዮፎኒ ። | ፴፫ | እግዚአብሔርም የነገራችሁን ቃል ሰምቶ ተቈጣ ለአባቶቻቸው የማልኩላቸው የተባረከች ያችን ምድር ከዮፎኒ ልጅ ከካሌብ በቀር እነዚህ ሰዎች እንዳያዩዋት ብሎ ማለ ። ዘኍ፡ ፲፬ ፳፪፡ መዝ፡ ፺፭ ፲፩ ። |
| ወውእቱ ይሬእያ ወሎቱ እሁብ ለይእቲ ምድር እንተ ውስቴታ ዐርገ ወለደቂቁ እስመ እምኀበ እግዚአብሔር ውእቱ ልቡ ። | ፴፬ | እሱ ያያታል (ይወርሳታል) የወጣባት ያችን አገር ለርሱ ለልጆቹም እሰጣታለሁ፥ ልቡናው ከእግዚአብሔር ጋር አንድ ሁኗልና ። ዘኍ፡ ፲፫ ፲፱፡ ኢያ፡ ፲፬ ፲፱ ። |
| ወኪያየኒ ተምዐኒ እግዚአብሔር በእንቲአክሙ ወይቤለኒ አንተኒ ኢትበውእ ህየ ። | ፴፭ | እኔንም እግዚአብሔር በናንተ ምክንያት ተቈጣኝ፥ አንተም ወደዚያ አትገባም አለኝ ። ዘኍ፡ ፳፯ ፲፬ ። |
| እስመ ኢያሱ ወልደ ነዌ ዘይቀውም ቅድሜከ ውእቱ ዘይበውእ ህየ ኪያሁ አጽንዖ ወውእቱ ያወርሶሙ ይእተ ምድረ ለእስራኤል ። | ፴፮ | በፊትህ የሚቆም የነዌ ልጅ ኢያሱ እርሱ ወደዚያ የሚገባ ነውና እሱን አጽናው ያችንም አገር እርሱ ለእስራኤል ያወርሳታል ። |
| ወደቂቅክሙ እለ ትቤሉ ይዴወዉ ወኵሉ ሕፃን ንኡስ ዘኢየአምር ዮም ሠናይተ ወእኪተ እሙንቱ ይበውኡ ህየ፥ ወሎሙ እሁብ ወእሙንቱ ይወርስዋ ። | ፴፯ | ይማረካሉ የምትሏቸው ልጆቻችሁ ክፉና በጎ ዛሬ የማያውቅ ሕፃን ሁሉ ትንሹም ሁሉ ወደዚያ ይገባሉ፥ ለነሱ እሰጣታለሁ፥ እነሱም ይወርሷታል ። |
| ወአንትሙሰ ተመየጡ ወገዐዙ ውስተ ገዳም ውስተ ፍኖተ ባሕረ ኤርትራ ። | ፴፰ | እናንተ ግን የኤርትራን ባሕር መንገድ ይዛችሁ ወደ ምድረ በዳ ተጓዙ ። ዘኍ፡ ፲፬ ፳፭፥ ዘዳ፡ ፪ ፩ ። |
| ወአውሣእክሙኒ ወትቤሉኒ አበስነ ቅድመ እግዚአብሔር አምላክነ ነዐርግ ንሕነ ወንትቃተል ወንገብር ኵሎ በከመ አዘዘነ እግዚአብሔር አምላክነ፥ ወነሣእክሙ ብእሲ ብእሲ ንዋየ ሐቅልክሙ ወዐረግሙ ውስተ ደብር ። | ፴፱ | ፈጣሪያችን እግዚአብሔርን በድለናልና፥ ፈጣሪያችን እግዚአብሔር እንዳዘዘን እኛም መጥተን እንዋጋለን ሁሉንም እናደርጋለን ብላችሁ መለሳችሁልኝ፥ አንዱም አንዱም ሰው ጋሻ ጦራችሁን ይዛችሁ ወደ ተራራው ወጣችሁ። |
| ወይቤለኒ እግዚአብሔር በሎሙ ኢትዕርጉ ወኢትትቃተሉ እስመ ኢሀለውኩ ምስሌክሙ ከመ ኢትትቀጥቀጡ ቅድመ ፀርክሙ ። | ፵ | እግዚአብሔርም በረድኤት ከናንተ ጋር የለሁምና በጠላቶቻችሁ ፊት እንዳትጠፉ ወጥታችሁ አትዋጉ በላቸው አለኝ ። ዘኍ፡ ፲፬ ፵፫፥ ፲፬ ፵ ። |
| ወነገርኩክሙ ወኢሰማዕክሙኒ ወተዐወርክሙ ቃለ እግዚአብሔር፥ ወተኀየልክሙ ወዐረግሙ ውስተ ደብር ። | ፵፩ | እኔም ነገርኋችሁ አልሰማችሁኝም የእግዚአብሔርን ቃል ቸል አላችሁ፥ ተበራትታችሁ ወደ ተራራ ወጣችሁ ። |
| ወወፅኡ አሞሬዎን እለ ይነብሩ ውስተ ውእቱ ደብር ወተቀበሉክሙ ወአንተዉክሙ ወሰደዱክሙ ወነደፉክሙ ከመ ንህብ ወወግኡክሙ እምሴይር እስከ ሔርማ ። | ፵፪ | በዚያው ተራራ የሚኖሩ የአሞሬዎን ሰዎች ወጥተው ተጋጠሙዋችሁ፥ ድል ነሥተውም አባረሩዋችሁ፥ እንደ ንብም እየነደፉ አሸሹአችሁ፥ ከሴይር እስከ ሔርማ ድረስ ወጋችሁ ። መዝ፡ ፻፲፰ ፱፥ ፻፲፰ ፲፪ ። |
| ወነበርክሙ ወበከይክሙ ቅድመ እግዚአብሔር ወኢሰምዐክሙ ቃለክሙ ወኢነጸረክሙ ። | ፵፫ | ተቀምጣችሁ በእግዚአብሔር ፊት አለቀሳችሁ፥ ነገር ግን ቃላችሁን አልሰማችሁም በምሕረትም አላያችሁም ። |
| ወነበርክሙ ውስተ ቃዴስ ብዙኀ መዋዕለ አምጣነ ነበርክሙ ቀዲሙ ። | ፵፬ | ቀድሞ የኖራችሁትን ያህል ብዙ ዘመን በቃዴስ ተቀመጣችሁ ። ዘኍ፡ ፳፩ ፳፬፥ መሳ፡ ፲፬ ፮ ። |
| ምዕራፍ ፪ ። | | ምዕራፍ ፪ ። |
| ወተመየጥነ ወሖርነ ውስተ ገዳም ፍኖተ ባሕረ ኤርትራ በከመ ይቤለኒ እግዚአብሔር ወዖድናሁ ለደብረ ሴይር ብዙኀ መዋዕለ ። | ፩ | እግዚአብሔር እንደ ነገረን ተመልሰን የኤርትራን ባሕር መንገድ ይዘን ወደ ምድረ በዳ ሄድን የሴይርንም ተራራ ብዙ ቀን (ዘመን) ዞርነው ። ዘኍ፡ ፲፱ ፳፭ ። |
| ወይቤለኒ እግዚአብሔር ከነክሙ ዐዊዶቱ ለዝንቱ ደብር ግብኡ እንከሰ ለመንገለ መስዕ ። | ፪ | እግዚአብሔር ይህን ተራራ መዞር በቃችሁ እንግዲህ ወዲህ ወደ ሰሜን ተመለሱ አለኝ ። ዘዳ፡ ፩ ፮ ። |

፫ ወአዝዞሙ ለሕዝብ ወበሎሙ ፡ ናሁ ተሐውሩ አንትሙ አንተ አድዋሊሆሙ ለአኃዊክሙ ደቂቀ ኤሳው እለ ይነብሩ ውስተ ምድረ ሴይር ወይፈርሁክሙ ጥቀ ።

፬ ውቁ ኢትትቃተሉ ምስሌሆሙ እስመ ኢይሁበክሙ እምድሮሙ ርስተ ወኢምሥጋረ እግር ፡ እስመ መክፈልቶ ወሀብክዎ ለኤሳው ደብረ ሴይር ።

፭ ወተሣየጡ እክለ እምኀቤሆሙ በወርቅክሙ ወተሴሰዩ ወማየኒ በመስፈርት ንሥኡ እምኀቤሆሙ በወርቅክሙ ወስትዩ ፡ እስመ በረከክሙ እግዚአብሔር አምላክክሙ በኵሉ ግብረ እደዊክሙ ።

፮ አእምር እፎ ዐደውከሁ ለዝንቱ ገዳም ዐቢይ ዘግሩም ውእቱ ፡ ናሁ አርባዓ ዓመ ሀለወ ምስሌከ እግዚአብሔር አምላክከ እንዘ አልቦ ዘያኀጥአከ እምኵሉ ዘነበብከ ።

፯ ወተዐደውናሆሙ ለአኀዊነ ደቂቀ ኤሳው እለ ይነብሩ ውስተ ሴይር ኀበ ፍኖተ ዓራብ እምኤሎም ወእምጋስዮን ጋቤር ወእምዝ ተመየጥነ ወዐደውነ ፍኖተ ገዳም ዘሞአብ ።

፰ ወይቤለኒ እግዚአብሔር ኢትፃረርዎሙ ለሞዓባውያን ወኢትትቃተሉ ምስሌሆሙ እስመ ኢይሁበክሙ ርስተ እምድሮሙ እስመ ለደቂቀ ሎጥ ወሀብክዎሙ ርስቶሙ ።

፱ ወዘሚን ቀዲሙ ነበሩ ውስቴታ ሕዝብ ዐበይት ጥቀ ወጽኑዓን ከመ እለ ውስተ አቂም ።

፲ ወራፋይን ከዐበ የኀድሩ እሙንቱኒ ከመ እለ ውስተ አቂም ፡ ወሞዓባውያን ዘሚን ይብልዎሙ ።

፲፩ ወኮሬዎስ ውስተ ሴይር ይነብሩ ቀዲሙ ወደቂቀ ኤሳው አጥፍእዎሙ ወቀጥቀጥዎሙ እምቅድመ ገጾሙ ወነበሩ በመካኖሙ ፡ ከማሁ ይገብርዎ እስራኤል ለምድረ ርስቶሙ ዘወሀቦሙ እግዚአብሔር ።

፲፪ ወይእዜኒ ተንሥኡ ወገዐዙ አንትሙ ወሑሩ ውስተ ቈላተ ዛሬድ ፡ ወተዐደውናሁ ለቈላተ ዛሬድ ።

፲፫ ወመዋዕሊሁ በዘዐቱ ግዕዝነ እምቃዴስ በርኔ እስከ ተዐደውናሁ ለቈላተ ዛሬድ ሠላሳ ወሰመንቱ ዓመት እስከ ሞቱ ኵሎሙ እደው ዘይእቲ ትውልድ እለ መስተቃትላን እሙንቱ ፡ ወጠፍኡ እማእከለ ትዕይንት በከመ መሐለ ላዕሌሆሙ እግዚአብሔር እግዚእ ።

፲፬ እስመ እደ እግዚአብሔር ሀለወት ላዕሌሆሙ ከመ ታጥፍአሙ እማእከላ ትእይንት እስከ ወድቁ ።

፲፭ ወኮነ እምዘወድቁ ኵሎሙ ውእቶሙ እደው መስተቃትላን ወሞቱ እማእከለ ሕዝብ ።

፲፮ ወነበበኒ እግዚአብሔር ወይቤለኒ ናሁ ተሐውሩ ወተዓድዉ ውስተ አድዋሊሆሙ ለሞዓብ ፡ ወትበጽሑ ቅሩበሙ ለደቂቀ አሞን ።

፲፯ ኢትፃረርዎሙ ወኢትትአኀዙ ቀትለ ምስሌሆሙ እስመ ኢይሁበክሙ ርስተ እምድሮሙ ለደቂቀ አሞን እስመ ለደቂቀ ሎጥ ወሀብክዎሙ መክፈልቶሙ ።

፲፰ ወይእቲ ምድረ ራፋይን ትሰመይ ፡ እስመ ራፋይን ይነብሩ ውስቴታ ቀዲሙ ፡ ወአሞናውያንኒ ዘሚን ይብልዎሙ ።

ሕዝቡን እንዲህ ብለህ እዘዛቸው ፤ በሴይር ወዳሉ ወደ ዔሳው ልጆች ወደ ወንድሞቻችሁ አውራጃ ሂዱ ፤ እነሳቸውም እጅግ ይፈሩዋቸኋል ። ዘኁ፡ ፳ ፲፬ ፡ ፳፩ ፡ ፳፩።

የሴይርን ተራራ ለዔሳው ዕጣ አድርጌ ስለ ሰጠሁት ፤ ከምድራቸው አንድ ጫማ ስንኳ አይሰጣችሁምና ከነርሱ ጋር እንዳትዋጉ ዕወቁ ። ዘፍ፡ ፴፫ ፩ ፡ ኢያ፡ ፳፬ ፬ ።

ከነሳቸው በወርቃችሁ እህል ሸምታችሁ ተመገቡ ፤ ውኃንም በመለኪያ ከነሳቸው በወርቃችሁ ገዝታችሁ ጠጡ ፤ ፈጣሪያችሁ እግዚአብሔር በእጃችሁ ሥራ ሁሉ ባርኳችኋልና (አከብሯችኋልና) ።

ጽኑ የሆነ የሚያስፈራ ይህን ምድረ በዳ እንዴት እንደዞርከው ከተናገርከው ሁሉ ፈጣሪህ እግዚአብሔር ያሳጣህ ሳይኖር ፵ ዘመን ካንተ ጋር በረድኤት እንደነበረ ዕወቅ ።

ከጋስዮን ጋቤርና ከኤሎም ተነሥተን በሴይር የሚኖሩ የዔሳው ልጆች ወንድሞቻችንን አልፈናቸው ወደ ዓራብ ጐዳና ሄድን ከዚህ በኋላ ተመልሰን በሞዓብ ምድረ በዳ ጐዳና አልፈን ሄድን ። ዘፍ፡ ፲፱ ፴፮ ።

እግዚአብሔር ለሎጥ ልጆች ርስት አድርጌ ስለ ሰጠኋቸው ከምድራቸው ምንም ርስት አይሰጣችሁምና ፤ የሞዓብን ልጆች አትጣሏቸው ከነሱ ጋር አትዋጉ አለኝ ።

በአቂም እንደነበሩ ሰዎች በጉልበት የጸኑ ፤ በቁመት የረዘሙ እጅግ ታላላቅና ብዙ ወገን የሚሆኑ ዘሚናውያን አስቀድሞ በውስጧ ነበሩ ። ዘኁ፡ ፲፫ ፪ ፡ ዘዳ፡ ፱ ፪ ።

በአቂም ኃይለኞች እንደ ነበሩ እነዚያ ኃይለኞችም ዳግመኛ ይኖሩበት ነበር ፤ የሞዓብም ሰዎች ዘሚን (ኃያላን) ይሏቸው ነበር ፤ (ራፋይን ረዣጅሞች) ። ዘፍ፡ ፬ ፭ ።

(ኮሬዎስ) ኃይለኞችም ቀድሞ በሴይር ይኖሩበት ነበር ፤ የዔሳው ልጆች ከፊታቸው ፈጽመው አጥፍተዋቸው በበታቸው ኖሩ ፤ እግዚአብሔር ርስት አድርጎ የሰጣቸው አገራቸውን የእስራኤል ልጆች እንደሱ ያድርጓት ።

አሁንም እናንተ ተነሥታችሁ ተጕዛችሁ ወደ ዛሬድ አውራጃ ሂዱ ፤ የዛሬድንም አውራጃ አልፈነው ሄድን ።

የዛሬድን ሸለቆ እስከ ተሻገርንበት ድረስ ጌታ እግዚአብሔር እንደ ማለባቸው እነዚያ ሰልፈኞች የዚያች ትውልድ ወገን የሆኑ ሰዎች ሁሉ እስኪ ጠፉ ድረስ ከቃዴስ በርኔ የተጓዝንበት ዘመን ሠላሳ ስምንት ዓመት ሆነ ።

ጨርሰው እስከ ጠፉ ድረስ ከሰፈር ለይታ ታጠፋቸው ዘንድ የእግዚአብሔር እደ መዓቱ በላያቸው ላይ ነበረችና ።

አርበኞች የሆኑ እነዚያ ሰልፈኞች ሁሉ ከሕዝቡ መካከል ተለይተው ሞተው ከጠፉ በኋላ እንዲህ ሆነ ።

እግዚአብሔርም እንዲህ ብሎ ተናገረኝ ፤ እነሆ የሞዓብን አውራጃ ተሻግራችሁ ትሄዳላችሁ ከአሞን ልጆችም አቅራቢያ ትደርሳላችሁ ። ዘፍ፡ ፲፱ ፴፰ ።

ለሎጥ ልጆች ዕጣ አድርጌ ስለ ሰጠኋቸው ከአሞን ልጆች ምድር ርስት አልሰጣችሁምና አትጣሏቸው ከነሱም ጋር ሰልፍ አትግጠሙ (አትዋጉ) ብሎ ነገረኝ ።

ቀድሞ (ራፋይን) ኃይለኞች ነበሩባትና ያችም አገር የኃይለኞች አገር ትባላለች ፤ አሞናውያን ግን ዘሚን (ኃያ

፭ ወለእመቦ ዘነሥአ ብእሲተ ግብተ ኢይፃእ ፀብአ ወኢ ፈልበ ምንትኒ ዘያቀትውዎ ድኑን ውእቱ ቤቱ አሐተ ዓመተ ከመ ይትፌሣሕ ምስለ ብእሲቱ እንተ አውሰበ ።

ድንገት ሚስት ያገባ ሰው ቢኖር ወደ ሰልፍ አይውጣ የዘመቻ ፈሬ ብለው ምንምን አያገብሩት ፤ ካገባት ሚስቱ ጋር ደስ ይለው ዘንድ ቤቱ አንድ ዓመት ከዘመቻ ፈሬ ይዳን ። ዘዳ፡ ፳ ፯፤ ምሳ፡ ፭ ፲፰ ።

፮ ወኢትእኀዝ ማሕረፀ ወኢመድሐ ማሕረፅ እስመ መብዕለ ነፍስ ውእቱ ወኢየአኀዝ ።

ወፍጮንና መጅን መያዣ አድርገህ አትያዝ፤ ሰውነት መመገቢያ ነውና አይያዙት ። ዘጸ፡ ፳፪ ፲፮ ።

፯ ወለእመቦ ዘተረክበ ብእሲ ዘሰረቀ ነፍሰ እምአኀዊሁ እምደቂቀ እስራኤል ወተሠገሎ ወሤጦ ፤ ለይቅትልዎ ለውእቱ ሰራቂ ወታሴስሉ እኩየ እምኔቲክሙ ።

ከወንድሞቹ ከእስራኤል ልጆች ሰውን የሰረቀ ቀምቶም የሸጠው ሰው ቢኖር ያን የሰረቀው ሰው ይግደሉት እንዲህ እያደረጋችሁ ከውስጣችሁ ክፉ ክፉውን አርቁ ።

፰ ወዑቅ ርእሰከ በእንተ ትእምርተ ለምጽ ተዓቀብ ጥቀ ከመ ትግበር ኵሎ ሕገ ዘይቤሉከ ካህናት ወሌዋውያን በከመ አዘዝኩከ ተዓቀብ ዘትገብር ።

ስለ ለምጽ ምልክት ለራስህ ዕወቅ፤ ሌዋውያንና ካህናት ያዘዙህን ሕጉን ሁሉ ትጠብቅ ዘንድ ፈጽመህ ተጠበቅ እንዳዘዝኩህ የምታደርገውን ጠብቅ ። ዘሌ፡ ፲፫ ፲፫ ።

፱ ወተዘከር ኵሎ ዘገብረ እግዚአብሔር አምላክከ ላዕለ ማርያ በፍኖት አመ ወፃእክሙ እምግብጽ ።

ከግብጽ በወጣችሁ ጊዜ ፈጣሪህ እግዚአብሔር በጉዳና በማርያ ያደረገውን ሁሉ አስብ ። ዘኁ፡ ፲፪ ፲ ።

፲ ወለእመቦ ዘይፈድየከ ካልእከ ዕዳ ዘከነ ኢትባእ ውስተ ቤቱ ከመ ተአኀዝ አኀዘከ ዳዕሙ አፍአ ትቀውም ።

በልንጀራህ የሚከፍለህ ዕዳ የሆነ ገንዘብ እንዳለ በውጭ ቁም እንጂ መያዣህን ትይዝ ዘንድ ወደ ቤቱ አትግባ።

፲፩ ወብእሲ ዕዳከ ዝክቱ ዘይፈድየከ ለሊሁ ያወፅእ አኀዘከ አፍአ ኀቤከ ።

ዕዳህን የሚከፍልህ ያ ሰው እሱ መያዣህን ከንተ ዘንድ ወደ ውጭ ያውጣልህ ።

፲፪ ወለእመ ብእሲ ነዳይ ውእቱ፤ ኢታቢት አኀዘ ኀቤከ ።

ያ ሰው ድኻ ቢሆን ግን፤ መያዣውን ከንተ ዘንድ አታሳድር ።

፲፫ ታገብእ ሎቱ አኀዘ ዘእንበለ ይዕርብ ፀሐይ ወይበይት በልብሱ ወትትባረክ ወይከውነከ ምጽዋተ በቅድመ እግዚአብሔር አምላክከ ።

ፀሐይ ሳይገባ መያዣውን መልስለት፤ ልብሱን ለብሶ ይደር አንተም ትመረቃለህ፤ በፈጣሪህ በእግዚአብሔርም ፊት ምጽዋት ይሆንልኻል ። ዘፀ፡ ፳፪ ፳፮ ።

፲፬ ወኢትፀምዮ ዐስበ ለዐሳብ ለነዳይ ዘኀጡእ ውእቱ እምአኀዊከ አው እምግዩራን ዘውስተ ሀገርከ ።

ከወንድሞችህ ወይም በአገርህ ካሉ ስደተኞች ገንዘብ ያጣ ድኻ ምንደኛ፤ ደመወዙን አትከዳው ።

፲፭ እንተ ጸብሐት ትሁብ ዐስቦ ወኢታዕርብ ፀሐየ ላዕሌሁ እስመ ነዳይ ውእቱ ወውእቱ ተሰፋሁ ወኢይግዐር ላዕሌከ ኀበ እግዚአብሔር ወኢይኩንከ ኀጢአተ ።

ድኻ ነውና አለኝታውም እሱ ነውና ወደ እግዚአብሔር እንዳይጮህብህ ኃጢአትም እንዳይሆንብህ ፀሐይ ሳይገባ በየቀኑ ደመወዙን ስጠው ። ዘሌ፡ ፲፱ ፲፫ ።

፲፮ ወኢይመውቱ ወላድያን በበይነ ውሉዶሙ ወኢይመውቱ ውሉዶሙ በበይነ ወላድያኒሆሙ አላ አሐዱ አሐዱ በጌጋዩ ይመውት ።

አንዱም አንዱም በበደለው በደል ይሞታል እንጂ፤ ወላጆች በልጆቻቸው ልጆችም በወላጆቻቸው በደል አይሞቱም ። ፬ ነገ፡ ፲፬ ፮፤ ሕዝ፡ ፲፰ ፳ ።

፲፯ ወኢትሚጥ ፍትሐ ግዩር ወዘእጓለ ማውታ ወዘዐቤር ።

እናት አባቱ የሞቱበትንና፤ የስደተኞችን፤ የባልቴትንም ፍርድ አትለውጥ ። ዘዳ፡ ፲ ፲፰፤ ኢሳ፡ ፩ ፳፫ ።

፲፰ ወተዘከር ከመ ገብር አንተ በምድረ ግብጽ ወቤዘወከ እግዚአብሔር አምላክከ እምህየ ወበበይነ ዝንቱ እኤዝዘከ አነ ትግበር ዘንተ ነገረ ።

በግብጽ አገር አንተ ተገዥ ባርያ እንደነበርህ ፈጣሪህ እግዚአብሔርም ከዚያ እንዳዳነህ አስብ፤ ስለዚህ ይህንን ታደርግ ዘንድ አዝሃለሁ ። ዘዳ፡ ፳፬ ፳፪፤ ፭ ፲፭ ።

፲፱ ወለእመ ዐፀድከ እክለ ገራህትከ ወረሳዕከ አሐተ ክልስስተ ውስተ ገራህትከ ኢትግባእ ከመ ትንሣእ፤ ለግዩር ወለእጓለ ማውታ ወለዐቤር ይኩን ከመ ይባርክ እግዚአብሔር አምላክከ በኵሉ ተግባረ እደዊከ ።

የእርሻህን አዝመራ ብታጭድ አንዲቱን ነዶ በእርሻህ ብትዘነጋ ታነሣት ዘንድ አትመለስ፤ ፈጣሪህ እግዚአብሔር በእጅህ ሥራ ሁሉ ያከብርህ ዘንድ እናት አባቱ ለሞቱበት ልጅና፤ ለስደተኛ፤ ለባልቴትም ይሁን ። ዘሌ፡ ፲፱ ፱ ።

፳ ወለእመኒ ቀሠምከ ዐፀደ ወይንከ ኢትድግም ተመይጠ ድኅሬከ ከመ ታስተናጽሕ ቀሢመ ለግዩር፤ ወለእጓለ ማውታ፤ ወለዐቤር ይኩን ።

የወይንህን ቦታ በቀሰምክ (በለቀምክ) ጊዜ፤ እጥርተህ ትለቅም ዘንድ ዳግመኛ ወደ ኋላህ አትመለስ፤ እናት አባቱ ለሞቱበት ልጅና፤ ለስደተኛ፤ ለባልቴትም ይሁን ።

፳፩ ወለእመኒ ቀሠምከ ዘይተከ ኢትድግም ተመይጠ ድኅሬከ ከመ ታስተናጽሕ ቀሢመ፤ ለግዩር፤ ወለእጓለ ማውታ ወለዐቤር ይኩን ።

እናት አባቱ ለሞቱበት ልጅና ለስደተኛ ለባልቴትም ይሁን እንጂ ዘይትህን በለቀምክ ጊዜ እጥርተህ ትለቅም ዘንድ ዳግመኛ ወደ ኋላህ አትመለስ ። ዘሌ፡ ፲፱ ፲ ።

፳፪ ወተዘከር ከመ ግዩር አንተ በምድረ ግብጽ ወቤዘወከ እግዚአብሔር አምላክከ እምህየ ።

አንተ በግብጽ ምድር ስደተኛ እንደ ነበርክ ፈጣሪህ እግዚአብሔርም ከዚያ እንዳዳነህ (እንዳወጣህ) አስብ ።

፳፫ ወበይነ ዝንቱ እኤዝዘከ አነ ትግበር ዘንተ ነገረ ።

ስለዚህም ይህንን ነገር ታደርግ ዘንድ እኔ አዝሃለሁ ።

| ምዕራፍ ፳፭ ። | | ምዕራፍ ፳፭ ። |
|---|---|---|
| ወለእመ ኮነ ተስናን በማእከለ ሰብእ ወመጽኡ ውስተ ዐውድ ወተሰነኑ ወአርትዑ ለዘይረትዕ ወአዕለዉ ለዘ ይጌጊ ። | ፩ | በሰዎች መካከል ጠብ ቢሆን፣ ሰዎችም ወደ ሸንጎ መጥተው ቢከራከሩ እውነቱን እውነት፣ ሐሰቱን ሐሰት ብላችሁ ፍረዱ ። ዘዳ፡ ፲፱ ፲፯ ፣ ምሳ፡ ፲፯ ፲፭ ። |
| ወለእመ ኮነ ለተቀሥፎ ያንብርዎ ቅድመ ዐውድ ለዝኩ ዘይጌጊ ወይቅሥፍዎ በቅድሜሆሙ በአምጣነ አበሳሁ ። | ፪ | በደሉም ሊመገረፍ ቢሆን ያን የሚገረፈውን ሰው በሸንጎ አስቀምጠው የበደለውን ያህል በፊታቸው ይግረፉት ። |
| አርባዓ ይቅሥፍዎ በኍልቈ ወኢያብዝኁ እምኔሁ ፤ ወለእመ አብዝኁ ቀሢፎቶ እምዝንቱ አስተኀፈርኮ ለእኁከ በቅድሜከ ። | ፫ | በቍጥር አርባ ይግረፉት፣ ከአርባ አትርፈው (አብዝተው) አይግረፉት፣ ከርባ አትርፈው ቢገርፉት ግን ወንድምህን በፊትህ አሳፈርከ (ነውረኛ አደረግህ) ። |
| ወኢትፍዕሞ አፉሁ ለላሕም ሶበ ታከይድ እክለ ። | ፬ | እኽልን በምታበራይበት ጊዜ የበሬውን አፉን አት ሰረው ። ፩ ቆሮ፡ ፱ ፱፣ ፩ ጢሞ፡ ፭ ፲፰ ። |
| ወለእመቦ አኀው እለ ይነብሩ ኅቡረ ብእሲ ምስለ እኁሁ ወሞተ አሐዱ እምኔሆሙ ወአልቦ ውሉድ ኢታውስብ ብእሲቱ ነኪረ ብእሴ እኁሁ ለምታ ለያውስባ ወው እቱ ለይባእ ኀቤሃ ወሎቱ ትኩኖ ብእሲቶ ወይንበር ምስሌሃ ። | ፭ | ወንድም ከወንድሙ ጋር አንድነት የሚኖሩ ወንድማ ማቾች ቢኖሩ ከነሳቸውም አንዱ ቢሞት ልጅ ባይኖረው የባሏ ወንድም ያግባት እንጂ ሚስቱ ሌላ ሰው አታግባ፤ እሱ ይድረስባት ለሱ ሚስት ትሁነው ከሷም ጋር ይኑር ። ሉቃ፡ ፳ ፳፰ ። |
| ወሕፃን ዘተወልደ ይኩን ለዘሞተ፣ ወይሰመይ በስሙ ወኢይደምሰስ ስሙ እምእስራኤል ። | ፮ | የተወለደውም ልጅ ለሞተው ሰው ይሁን ከእስራኤል ስሙ እንዳይጠፋም በስሙ ይጠራ ። ዘፍ፡ ፴፰ ፱ ። |
| ወለእመ ኢፈቀደ ውእቱ ብእሲ ያውስባ ለብእሲተ እ ኁሁ ፣ ወተዐርግ ይእቲ ብእሲት ኀበ ሊቃናት ወኀበ አን ቀጽ ወትብል ኢይፈቅድ እኁሁ ለምትየ ያቅም ስመ እኁ ሁ ውስተ እስራኤል ። | ፯ | ያ ሰው የወንድሙን ሚስት ሊያገባት ባይወድ ግን ያች ሴት በአደባባይ ወዳሉ ሽማግሌዎች ወጥታ የባሌ ወን ድም በእስራኤል ዘንድ የወንድሙን ስም ያስጠራ ዘንድ አልወደደም ትበል ። ሩት ፩ ፲፭ ፣ ፬ ፪ ። |
| ይጸውዕዎ ሊቃናተ ሀገር ወይበልዎ ኢትፈቅዶኑ ታቅ ም ዘርአ ለእኁከ ውስተ እስራኤል ወይበል ቀዊሞ ኢይ ፈቅድ አውስቦ ። | ፰ | የአገር ሽማግሌዎችም ጠርተው በእስራኤል መካከል ለወንድምህ ልጅ ልትተክ አትወድምን፤ ይበሉት፣ እሱም ቁሞ ላገባት አልወድም ይበል ። ሩት ፬ ፯ ። |
| ወትቅረብ ይእቲ ብእሲት ኀቤሁ ቅድመ ሊቃናተ ይ እቲ ሀገር ወትፍታሕ ሣእኖ ዘእሐቲ እግሩ ወትትፋእ ውስ ተ ገጹ ወትብል ከመዝ ይግበርዎ ለብእሲ ዘኢይፈቅድ ይሕንጽ ቤተ እኁሁ ። | ፱ | ያችም ሴት በዚያች አገር ሽማግሌዎች ፊት ወደርሱ ቀርባ ያንዲት እግሩ ጫማ ፈትታ ምራቋን እንትፍ ትበል በት፤ የወንድሙን ቤት ይሠራ ዘንድ የማይወደውን ሰው እንዲህ ያድርጉት ትበል ። ዘኍ፡ ፲፪ ፲፬ ፣ ሩት ፬ ፯ ። |
| ወይሰመይ ስሙ በውስተ እስራኤል ቤተ ፍቱሐ አሣእን ። | ፲ | ስሙም በእስራኤል ዘንድ ጫማው የወለቀ ሰው ወገን ይባል ። ምሳ፡ ፯ ፴፫ ፣ ፩ ጢሞ፡ ፫ ፯ ። |
| ወለእመ ተባአሱ ክልኤቱ እደው ኅቡረ ብእሲ ምስለ ካልኡ ወመጽአት ብእሲቱ ለአሐዱ እምኔሆሙ ከመ ታኅ ድጎ ለምታ እምእደ ዘበጠሁ ወአልዐለት እዴሃ ወአኀዘቶ በክልኤሆን አስከቲሁ ለይምትሩ እዴሃ ወኢትምሐክ ዐይንከ ። | ፲፩ | ሁለት ሰዎች አንዱ ካንዱ ጋራ አንድነት ቢጣሉ ባሏን ከሚመታው ሰው እጅ ታስጥለው ዘንድ ከነሱ ያንዱ ሰው ሚስት መጥታ እጅዋን ዘርግታ ሁለት ብልቶቹን ብትይ ዘው እጅዋን ይቍረጧት፣ ዓይንህም አትራራላት ። ዘዳ፡ ፲፱ ፲፫ ። |
| ወኢታንብር ለከ መዳልወ ንኡሰ ወዐቢየ ወኢትግበር ለከ በውስተ ቤትከ መስፈርተ ንኡሰ ወመስፈርተ ዐቢየ ። | ፲፪ | ላንተ ታላቅ ሚዛንና ታናሽ ሚዛን ታላቅ ቁናና ታናሽ ቁና በቤትህ አታኑር ። ምሳ፡ ፲፮ ፲፩ ፣ ሚክ፡ ፮ ፲፩ ። |
| መዳልውከኒ ርቱዐ ወጽዱቀ ይኩንከ ከመ ታብዝኅ መዋዕለ በምድር ዘይሁበከ እግዚአብሔር አምላክከ ርስተ ። | ፲፫ | ፈጣሪህ እግዚአብሔር ርስት አድርጎ በሚሰጥህ ምድ ር ዕድሜህ ይረዝም ዘንድ፣ ሚዛንህ የቀናና እውነተኛ ይሁን ። ምሳ፡ ፲፩ ፩ ። |
| እስመ ርኩስ ውእቱ በኀበ እግዚአብሔር አምላክከ ኵሉ ዘይገብሮ ለዝንቱ ወኵሉ ዘይገብር ዐመፃ ። | ፲፬ | ይህን የሚያደርግ ሰው ሁሉ በደልንም የሚያደርግ ሁሉ በፈጣሪህ በእግዚአብሔር ዘንድ የተጠላ ነውና ። |
| ወተዘከር ኵሎ ዘገብረ ላዕሌከ አማሌቅ በፍኖት አመ ወፃእከ እምድረ ግብጽ ። | ፲፭ | ከግብጽ አገር በወጣህ ጊዜ አማሌቅ በጐዳና ያደረገ ብህን ሁሉ አስብ ። ዘፀ፡ ፲፯ ፰ ፣ ዘዳ፡ ፳፬ ፱ ። |
| ዘከመ ተቃወመከ በፍኖት ወአምተረከ ጋዕዘከ እለ ይደክሙ በድኅሬከ ። | ፲፮ | በጐዳናም እንዴ ተቃወመህ ካንተ በኋላ ደክመው የነ በሩትን ጓዞችህንም ነጥቆ እንዳስቀረ አስብ ። |

| | | |
|---|---|---|
| ወአንተሰ ርኅብከ ወደከምከ ወኢፈራህኮ ለእግዚአብሔር አምላክከ ። | ፲፰ | አንተም ደክሞህ ርቦህ ሳለ ፈጣሪህ እግዚአብሔርን አልፈራኸውም ። ኢያ፣ ፲ ፲፱፣ ፪ ሳሙ፣ ፲፯ ፪ ። |
| ወአመ ያዐርፈከ እግዚአብሔር አምላክከ እምኵሉ ፀርከ ዘዐውድከ ውስተ ምድር ዘይሁበከ እግዚአብሔር አምላክከ ትትዋረሳ ርስተ ትደመስሶ ለአማሌቅ እምታሕተ ሰማይ ወኢትረስዖ ። | ፲፱ | ርስት አድርገህ ትወርሷት ዘንድ ፈጣሪህ እግዚአብሔር በሚሰጥህ ምድር በዙርያህ ካሉ ጠላቶችህ ሁሉ ፈጣሪህ እግዚአብሔር ባሳረፈህ ጊዜ አማሌቅን ከሰማይ በታች አጥፋው፤ አትዘንጋው ። ዘፀ፡ ፲፯ ፲፬ ። |
| **ምዕራፍ ፳፮ ።** | | **ምዕራፍ ፳፮ ።** |
| ወለአመ ቦእከ ውስተ ምድር ዘይሁበከ እግዚአብሔር አምላክከ ትትዋረሳ ርስተ ወነበርከ ውስቴታ ትነሥእ እምፍሬ ምድር ዘወሀበከ እግዚአብሔር አምላክከ ። | ፩ | ርስት አድርገህ ትወርሳት ዘንድ ፈጣሪህ እግዚአብሔር ወደ ሚሰጥህ ምድር ብትገባ በውስጧም ብትኖር፣ ፈጣሪህ እግዚአብሔር ከሰጠህ ምድርህ የተገኘውን ፍሬ ውሰድ ። ምሳ፡ ፫ ፱፣ ሮሜ ፰ ፳፫ ። |
| ወትወዲ ውስተ ቀርጠሉን ወተሐውር ውስተ መካን ዘኀረየ እግዚአብሔር አምላክከ ከመ ይሰመይ ስሙ በህየ ። | ፪ | በአገልግልም ይዘህ በዚያ ስሙ ይጠራበት ዘንድ ፈጣሪህ እግዚአብሔር ወደ መረጠው ቦታ ሂድ ። |
| ወትበውእ ኀበ ካህን ዘሀለወ በውእቱ መዋዕል ወትብሎ እየድዕ ዮም ቅድመ እግዚአብሔር አምላኪየ እስመ በጻሕኩ ውስተ ምድር ዘመሐለ እግዚአብሔር ለአበዊነ ከመ የሀበነ ። | ፫ | በዚያ ወራት ወዳለውም ካህን ገብተህ እኛን ይሰጠን ዘንድ እግዚአብሔር ላባቶቻችን ወደ ማለላቸው ምድር ደረሽለሁና አሁን በፈጣሪዬ በእግዚአብሔር ፊት እናገራለሁ በለው ። |
| ወይነሥእ ካህን ለውእቱ ሙዳየ ቀርጠሉን እምውስተ እደዊከ ወያነብሮ ቅድመ ምሥዋዑ ለእግዚአብሔር አምላክከ ። | ፬ | ካህኑም ያንን አገልግል ከእጅህ ተቀብሎ በፈጣሪህ በእግዚአብሔር መሠውያ ፊት ያኑረው ። ሆሴዕ ፲፪ ፲፪ ። |
| ወትብል ቅድመ እግዚአብሔር አምላክከ አበውየ ወፅኡ እምድረ ሶርያ ወወረዱ ውስተ ግብጽ ወነበሩ ህየ እንዘ ውኁዳን እሙንቱ በኍልቌሆሙ ወኮኑ በህየ ሕዝበ ዐቢየ ወመልኡ ወዐብዩ ብዙኀ ። | ፭ | አባቶቼ በእግዚአብሔር ትእዛዝ ከሶርያ ምድር መጥተው ወደ ግብጽ ወረዱ፤ እነሱም በቍጥራቸው ጥቂት ሁነው ሳሉ በግብጽ ኖሩ፤ በዚያም ታላቅ ወገን ሆኑ፤ በዓለም መሉ፤ እጅግም በዙ ። ዘፍ፡ ፵፫ ፪ ። |
| ወሣቀዩነ ግብጽ ወአሕመሙነ ወአገበሩነ ዕፁበ ግብረ ። | ፮ | ግብጻውያንም መከራ አጸኑብን አስጨነቁን የሚያስጨንቅም ሥራ አሠሩን ። ዘፀ፡ ፲፩ ፲፬ ። |
| ወጸራሕነ ኀበ እግዚአብሔር አምላከ አበዊነ ወሰምዐ እግዚአብሔር ቃለነ ወርእየ ሕማመነ ወሥራሐነ ወሥቃየነ ። | ፯ | እኛም ወደ አባቶቻችን ፈጣሪ ወደ እግዚአብሔር ጮኸን፤ እግዚአብሔርም ድካማችንንና መከራችንን አይቶ ልመናችንን ሰማን ። ዘፀ፡ ፪ ፳፫ - ፳፭ ። |
| ወአውፅአነ ለሊሁ እምድረ ግብጽ በእድ ጽንዕት ወበመዝራዕት ልዑል በዐቢይ ግርማ ወበዓቢይ ተአምር ወመድምም ። | ፰ | እሱ በጸናች ሥልጣንና በተዘረጋች ክንድ በታላቅ መፈራት በታላቅና በድንቅ በድንቅ ተአምራት ከግብጽ አገር አወጣን ። ዘፀ፡ ፲፪ ፴፯፣ ዘዳ፡ ፬ ፴፬ ። |
| ወአብአነ ውስተ ዝንቱ መካን ወወሀበናሃ ለዛቲ ምድር እንተ ትውኅዝ ሐሊበ ወመዓረ ። | ፱ | ማርና ወተት የምታፈሰውን ይህችንም ምድር ሰጥቶ ወደዚህ ቦታ አገባን ። ዘፀ፡ ፫ ፰፣ ዘዳ፡ ፳፮ ፲፭ ። |
| ወይእዜኒ ናሁ አምጻእኩ ቀዳሚ እክለ ምድርየ ዘወሀበኒ እግዚአብሔር ምድረ እንተ ትውኅዝ ሐሊበ ወመዓረ ወትሰግድ ቅድመ እግዚአብሔር አምላክከ ። | ፲ | አሁንም እግዚአብሔር ከሰጠኝ ማርና ወተት ከምታፈሰው ምድር የምድሬን እኽል መጀመሪያ እነሆ አመጣሁ በፈጣሪህ በእግዚአብሔር ፊት ስገድ ። |
| ወትትፌሣሕ በኵሉ በረከት ዘወሀበከ እግዚአብሔር አምላክከ አንተ ወቤትከ ወሌዋዊኒ ወግዩርኒ ዘኀቤከ ። | ፲፩ | ፈጣሪህ እግዚአብሔር በሰጠህ በረከት ሁሉ አንተን ደስ ይበልህ፤ ወገንህንም ካህንም በአንተ ዘንድ ያለ ስደተኛውንም ደስ ይበለው ። ዘዳ፡ ፲፪ ፯ ። |
| ወእምከመ ፈጸምከ ዐሥሮተ ኵሉ ዐሥራት ዘእክለ ኵሉ ምድርከ በሣልስ ዓም፤ ወእምዝ ዘአመ ዳግም ትዔሥር ክልኤተ ዓሥራተ ወትሁብ ለሌዋዊ ወለግዩርኒ ወለእጓለ ማውታ ወለዕቤር ይብልዕዎ በሀገርከ ወይጽገቡ ። | ፲፪ | በሦስተኛው ዓመት ከመሬትህ ከተገኘው እኽል አሥራት አውጥተህ በጨረስክ ጊዜ ከዚህ በኋላ ሁለተኛ አሥራት አውጥተህ ለካህኑ፣ ለስደተኛው፣ ለባልቴትና፣ እናት አባቱ ለሞቱበትም ልጅ ስጠው፤ በአገርህም በልተው ይጥገቡ ። ዘሌ፡ ፳፯ ፴፣ ዘዳ፡ ፲፬ ፳፱ ። |
| ወትብል በቅድመ እግዚአብሔር አምላክከ አንጻሕኩ ዘእዌድስ ለከ እምነ ቤትየ ወወሀብክዎ ለሌዋዊ ወለግዩር | ፲፫ | በፈጣሪህ በእግዚአብሔር ፊት ከገንዘቤ ለይቼ ለስደተኛና ለካህን ለባልቴትና እናት አባቱ ለሞቱበት ልጅ አን |

በር ኵሎ ትእዛዞ ወኵነኔሁ ዘአነ እኤዝዘከ ዮም ።

፱ ወአዘዞሙ ሙሴ ለሕዝብ በይእቲ ዕለት ወይቤሎሙ እሉ እሙንቱ እለ ይቀውሙ ወይባርክዎ ለሕዝብ በደብረ ገሪዛን ዓዲወኪሙ ዮርዳኖስ ፡ ስምዖን ወሌዊ ፡ ወይሁዳ ፡ ወይሳኮር ፡ ወዮሴፍ ፡ ወብንያም ።

፲ ወእሉ እሙንቱ እለ ይቀውሙ ለረጊም በደብረ ጌባል ሮቤል ፡ ወጋድ ፡ ወአሴር ፡ ወዛብሎን ፡ ወዳን ፡ ወንፍታሌም ።

፲፩ ወያወሥኡ ሌዋውያን ወይብልዎሙ ለኵሉ እስራኤል በዐቢይ ቃል ።

፲፪ ርጉም ለይኩን ብእሲ ዘይገብር ግልፎ ወስብከ ዘርኩስ በኀበ እግዚአብሔር ግብረ ኬንያ ፡ ወዘይሠይም ወየኀብእ ወያወሥኡ ፡ ኵሉ ሕዝብ ወይብሉ አሜን ወአሜን ።

፲፫ ርጉም ለይኩን ዘያስተሐቂ አባሁ ወእሞ ፡ ወይብሉ ኵሉ ሕዝብ አሜን ወአሜን ።

፲፬ ርጉም ለይኩን ዘይሰርቅ ደወለ ቢጹ ፡ ወይብሉ ኵሉ ሕዝብ አሜን ወአሜን ።

፲፭ ርጉም ለይኩን ዘያስሕቶ ፍኖተ ለዕዉር ፡ ወይብሉ ሕዝብ አሜን ወአሜን ።

፲፮ ርጉም ለይኩን ዘይጌምፅ ፍትሐ ግዩር ወዘእጓለ ማውታ ወዘዐቤር ፡ ወይብሉ ኵሉ ሕዝብ አሜን ወአሜን ።

፲፯ ርጉም ለይኩን ዘይሰክብ ምስለ ብእሲተ አቡሁ እስመ ከሠተ ኀፍረተ አቡሁ ፡ ወይብሉ ኵሉ ሕዝብ አሜን ወአሜን ።

፲፰ ርጉም ለይኩን ዘይሰክብ ምስ ኵሉ እንስሳ ፡ ወይብሉ ኵሉ ሕዝብ አሜን ወአሜን ።

፲፱ ርጉም ለይኩን ዘይከብ ምስለ እኅቱ እመኒ እንተ እም አቡሁ ፡ ወእመኒ እንተ እምእሙ ፡ ወይብሉ ኵሉ ሕዝብ አሜን ወአሜን ።

፳ ርጉም ለይኩን ዘይሰክብ ምስለ እመ ብእሲቱ ፡ ወይብሉ ኵሉ ሕዝብ አሜን ወአሜን ።

፳፩ ርጉም ለይኩን ዘይዘብጦ ካልኦ በነገረ ጕሕሉት ፡ ወይብሉ ኵሉ ሕዝብ አሜን ወአሜን ።

፳፪ ርጉም ለይኩን ዘይነሥእ ሕልያነ ከመ ይቅትል ነፍሰ ወደመ ንጹሐ ፡ ወይብሉ ኵሉ ሕዝብ አሜን ወአሜን ።

፳፫ ርጉም ለይኩን ኵሉ ብእሲ ዘኢይቀውም ይግበር ቃለ ዘውስተ ዝንቱ ሕግ ፡ ወይብሉ ኵሉ ሕዝብ አሜን ወአሜን ።

ምዕራፍ ፳፰ ።

፩ ወእመ ሰሚዐ ሰማዕከ ቃለ እግዚአብሔር አምላክከ ወዐቀብከ ከመ ትግበር ኵሎ ትእዛዞ ዘአነ እኤዝዘከ ዮም ይሬስየከ እግዚአብሔር አምላክከ መልዕልተ ኵሉ አሕዛበ ምድር ።

፪ ወይበጽሐከ ዝንቱ ኵሉ በረከት ወይረክበከ ለእመ ሰማዕከ ቃለ እግዚአብሔር አምላክከ ።

ዛሬ የማዝህን ትእዛዙንና ፍርዱን ሁሉ አድርግ አላቸው ።

ሙሴ በዚያች ቀን ሕዝቡን እንዲህ ብሎ አዘዛቸው ፡ ዮርዳኖስን በተሻገራችሁ ጊዜ ገሪዛን በሚባል ተራራ ላይ ቆመው ሕዝቡን የሚመርቁት እሊህ ናቸው ፤ ስምዖን ፡ ሌዊ ፡ ይሁዳ ፡ ይሳኮር ፡ ዮሴፍና ብንያም ናቸው ።

ለመርገምም በጌባል ተራራ የሚቆሙ እሊህ ናቸው ፤ ሮቤል ፡ ጋድ ፡ ዛብሎን ፡ አሴር ፡ ንፍታሌምና ዳን ናቸው ።

እነዚያ ሌዋውያንም ለእስራኤል ሁሉ በታላቅ ቃል እንዲህ ብለው ይመልሱላቸዋል ።

በእግዚአብሔር ዘንድ የተጠላ (ርኩስ የሆነ) የተቀረጸ ጣኦትን የሚያደርግ ሰው ሠራሽ ጣኦትንም ሠውሮ የሚያኖር ሰው የተረገመ ይሁን ይበሉዋቸው ፡ ሕዝቡም ሁሉ መልሰው (አሜን) ይሁን ይሁን ይበሉ ። ዘፀ፡ ፳ ፬ ።

እናት አባቱን የሚያቃልል ሰው የተረገመ ይሁን ፡ ይበሉዋቸው ሕዝቡም ሁሉ መልሰው ይሁን ይሁን ይበሉ ።

የባልንጀራውን ድንበር የሚሰርቅ (የሚያፈርስ) ሰው የተረገመ ይሁን ይበሏቸው ፡ ሕዝቡም ሁሉ መልሰው ይሁን ይሁን ይበሉ ።

ዕውሩን ጐዳና የሚያስተው የተረገመ ይሁን ይበሏቸው ፡ ሕዝቡም ሁሉ መልሰው ይሁን ይሁን ይበሉ ።

እናት አባቱ በሞቱበት ልጅ ፡ በመጻተኛና ፡ በበልቴትም ፍርድ የሚያደላ ሰው የተረገመ ይሁን ይበሏቸው ፡ ሕዝቡም ሁሉ መልሰው ይሁን ይሁን ይበሉ ።

ያባቱን ኀፍረት ገልጧልና ከእንጀራ እናቱ የደረሰ ሰው የተረገመ ይሁን ይበሏቸው ፡ ሕዝቡም ሁሉ መልሰው ይሁን ይሁን ይበሉ ። ዘሌ፡ ፲፰ ፰ ፡ ዘዳ፡ ፳፪ ፴ ።

በእንስሳም የሚደርስ ሁሉ የተረገመ ይሁን ይበሉዋቸው ፡ ሕዝቡም ሁሉ ይሁን ይሁን ይበሉ ።

ከባቱ የተወለደች ወይም ከናቱ ከተወለደች ከእኅቱ የደረሰ ሰው የተረገመ ይሁን ይበሏቸው ፡ ሕዝቡም ሁሉ ይሁን ይሁን ይበሉ ። ዘሌ፡ ፲፫ ፱ ፡ ፳ ፲፯ ።

በሚስቱ እናት በማቱ የሚደርስ ሰው የተረገመ ይሁን ይበሏቸው ፡ ሕዝቡም ሁሉ ይሁን ይሁን ይበሉ ።

በሥውር ባልንጀራውን የሚመታ ሰው የተረገመ ይሁን ይበሏቸው ፡ ሕዝቡም ሁሉ ይሁን ይሁን ይበሉ ።

ነፍስን ለመግደል ንጹሕ ደምንም ለማፍሰስ ማማለጃ (ጉቦ) የሚቀበል ሰው የተረገመ ይሁን ይበሏቸው ፡ ሕዝቡም ሁሉ ይሁን ይሁን ይበሉ ። ዘፀ፡ ፳፫ ፰ ።

በዚህ ሕግ ያለውን ቃል ያደርግ ዘንድ የማይጸና ሰው የተረገመ ይሁን ይበሏቸው ፡ ሕዝቡም ሁሉ ይሁን ይሁን ይበሉ ። ዘዳ፡ ፳፰ ፲፭ ፡ ኤር፡ ፲፩ ፫ ። ገላ፡ ፫ ፲ ።

ምዕራፍ ፳፰ ።

የፈጣሪህ የእግዚአብሔርን ቃል መስማትን ብትሰማ፡ እኔም አሁን የማዝህን ትእዛዙን ሁሉ ታደርግ ዘንድ ሕጉን ብትጠብቅ ፈጣሪህ እግዚአብሔር በምድር ካሉ ከአሕዛብ ሁሉ በላይ ያደርግሃል ። ዘፀ፡ ፲፭ ፳፮ ፡ ዘሌ፡ ፳፮ ፫ ።

የፈጣሪህ የእግዚአብሔርን ቃል ከሰማህ (ይህ ሁሉ ምርቃት ይደርስብሃል) ይደረግልሃል ። ዘዳ፡ ፳፰ ፲፭ ።

፫ ቡሩክ ትከውን በሐቅል ፡ ወቡሩክ ትከውን በሀገር ።

፬ ብሩክ ይከውን ፍሬ ከርሥከ ፡ ወቡሩክ ይከውን እክለ ምድርከ ወቡሩክ ይከውን መራዕየ አብግዒከ ወአልሕምቲከ ።

፭ ቡሩክ ይከውን መዛግብቲከ ወትራፋቲከ ።

፮ ቡሩክ ትከውን በበአትከ ፡ ወቡሩክ ትከውን በበአትከ ።

፯ ወያገብኦሙ እግዚአብሔር አምላክከ ውስተ እዴከ ለፀርከ ከመ ይትቀጥቀጡ በታሕተ እገሪከ ፡ በአሐቲ ፍኖት ይወፅኡ ይትቀበሉከ ፡ ወበሰብዑ ፍናው ይነትዑ እምቅድመ ገጽከ ።

፰ ወይፈኑ እግዚአብሔር በረከቶ ውስተ አብያቲከ ወውስተ ኵሉ ዘወደይከ እዴከ በውስተ ምድር ዘወሀበከ እግዚአብሔር አምላክከ ።

፱ ወያቀውመከ እግዚአብሔር ሎቱ ሕዝበ ቅዱሰ በከመ መሐለ እግዚአብሔር ለአበዊከ ፡ ለእመ ሰማዕከ ቃለ እግዚአብሔር አምላክከ ወሖርከ በፍናዊሁ ።

፲ ወይሬእዩ ኵሉ አሕዛበ ምድር ከመ ተሰምየ ላዕሌከ ስሙ ለእግዚአብሔር አምላክከ ወይፈርሁከ ።

፲፩ ወያስተበዝኀከ እግዚአብሔር አምላክከ ውስተ ሠናይት በውሉደ ከርሥከ ወበእክለ ምድርከ ።

፲፪ ወያስተዋልዶን ለእንስሳከ በውስተ ምድር ዘመሐለ እግዚአብሔር አምላክከ ለአበዊከ ከመ የሀብከ በከመ መዋዕለ ሰማይ ዲበ ምድር ።

፲፫ ወይፈትሕ ለከ እግዚአብሔር መዝገበ ቡሩከ ፡ ሰማየ ከመ የሀብከ ዝናመ በመዋዕሊሁ ለምድርከ ፡ ከመ ይባርክ ለከ ኵሎ ተግባረ እደዊከ ወትሌቅሕ አንተ ለብዙኃን አሕዛብ ወአንተሰ ኢትትሌቃሕ ፡ ወትኴንኖሙ አንተ ለብዙኃን አሕዛብ ፡ ወለከሰ ኢይኴንኑከ ።

፲፬ ወይሠይመከ እግዚአብሔር ውስተ ርእስ ወአኮ ውስተ ዘነብ ፡ ወትከውን መልዕልተ ወኢትከውን መትሕተ ፡ ለእመ ሰማዕከ ቃለ እግዚአብሔር አምላክከ ወትእዛዘ ኵሎ ዘአነ እኤዝዘከ ዮም ከመ ትዕቀብ ወትግበር ።

፲፭ ወኢትትገኃሥ እምኵሉ ቃል ዘአነ እኤዝዘከ ዮም ኢለየማን ወኢለፀጋም ፡ ከመ ትሖር ድኅረ አማልክተ ባዕድ ታምልኮሙ ።

፲፮ ወለእመሰ ኢሰማዕከ ቃለ እግዚአብሔር አምላክከ ከመ ትዕቀብ ኵሎ ትእዛዞ ዘአነ እኤዝዘከ ዮም ይመጽኣ ላዕሌከ ኵሉ ዝንቱ መርገም ወይረክበከ ።

፲፯ ወትከውን ርጉመ አንተ በሐቅል ወበሀገር ።

፲፰ ወይከውን ርጉመ መዛግብቲከ ወትራፋቲከ ።

፲፱ ወርጉመ ይከውን ፍሬ ከርሥከ ወእክለ ምድርከ ወመራዕየ አልሕምቲከ ወአባግዒከ ።

፳ ወርጉም አንተ በበአትከ ፡ ወበፀአትከ ።

፳፩ ወይፌኑ እግዚአብሔር ላዕሌከ ንዴተ ወረኃበ ወብድብደ ወይጠፍእ ኵሉ ዘወደይከ እዴከ ውስቴቱ ወይሜር

በከተማም በበረሃም የተባረክህ የተመረቅህ ትሆናለህ፤

የሆድህም ፍሬ (ልጅህ) የተመረቀ ይሆናል ከምድርህ የተገኘ አዝመራህም የተባረከ ይሆናል የበጎችህም የላሞችህም መንጋ የተባረከ ይሆናል ። ዘዳ፡ ፲፩ ፲፰ ፡ ፯ ፫ ።

ድልብህና ገንዘብህም የተባረከ ይሆናል ።

በመግባትህና በመውጣትህም የተመረቅህ ትሆናለህ ።

ፈጣሪህ እግዚአብሔርም ከእግርህ በታች ይወድቁ ዘንድ ጠላቶችህን በእጅህ ይጥልልሃል ፡ ይቀበሉህም ዘንድ በአንድ መንገድ ይመጡብሃል ፡ በሰባትም ጐዳና ከፊትህ ይሸሻሉ ።

እግዚአብሔርም በቤትህ በረከቱን ይልክልሃል ፡ ፈጣሪህ እግዚአብሔር በሰጠህ ምድር በእጅህ በያዝከው ገንዘብህ ሁሉ በረከቱን ያሳድራል ። ዘሌ፡ ፳፭ ፳፩ ።

ፈጣሪህ የእግዚአብሔርን ቃል ከሰማህ ፡ በሕጉም ጸንተህ ከኖርህ እግዚአብሔር ለአባቶችህ እንደማለ ለሱ የተለየህ ወገን አድርጎ ያቆምሃል ። ዘፀ፡ ፲፱ ፮ ።

በዚህ ዓለም ያሉ አሕዛብም ሁሉ የፈጣሪህ የእግዚአብሔር ስም በአንተ እንደ ተጠራ አይተው ይፈሩሃል ።

ፈጣሪህ እግዚአብሔርም ከአብራክህ በተከፈሉ ልጆችህ ከምድርህም በተገኘው አዝመራ በበጎ ረድኤት የብዙ ብዙ ያደርግሃል ። ምሳ፡ ፲ ፳፪ ።

ጠፈር በአድማስ ጸንቶ እንዲኖር ለአባቶችህ እንደ ማለላቸው ፈጣሪህ እግዚአብሔር በዚህ ዓለም አጽንቶ ያኖርህ ዘንድ ከብቶችህም እንዲዋለዱ ያደርጋቸዋል ።

ምድርህ በምታበቅልበት ወራት ሰማይ ዝናም ለዘር ይሰጥህ ዘንድ ፡ የእጅህንም ሥራ ሁሉ ይባርክልህ ዘንድ እግዚአብሔር መልካሙን መዝገብ ሰማዩን ይከፍትልሃል ፡ አንተ ለብዙ አሕዛብ ታበድራለህ ፡ አንተ ግን አትበደርም አንተ ብዙ አሕዛብን ትገዛቸዋለህ ፡ አንተን ግን አይገዙህም ። ፪ ነገ፡ ፳፪ ፪ ፡ ምሳ፡ ፬ ፳፯ ።

ዛሬ እኔ የማዝህን የፈጣሪህ የእግዚአብሔርን ቃል ብትሰማ ትእዛዙንም ብትጠብቅና ብትፈጽም ፡ እግዚአብሔር ራስ ያደርግሃል እንጂ ፡ ጅራት (ገዥ ያደርግሃል እንጂ ተገዥ) አያደርግህም ። ኢያ፡ ፩ ፯ ።

ታመልካቸው ዘንድ የአሕዛብን ጣኦታት በትከተልና እኔ ዛሬ ከዘዝኩህም ቃል ወደ ቀኝ ወደ ግራ ብትል ፡ ከሁሉ በላይ ትሆናለህ እንጂ ከሁሉ በታች አትሆንም ።

እኔ አሁን የማዝህን ትእዛዙን ሁሉ ትጠብቅ ዘንድ የፈጣሪህ የእግዚአብሔርን ቃል ብትሰማ ግን ይህ ሁሉ ርግማን ይደርስብሃል ፡ መከራም ያገኝሃል ።

አንተ በከተማም በበረሃም የተረገምክ ትሆናለህ ።

ድልብህም ገንዘብህም የተረገመ ይሆናል (ይጠፋል) ።

ከአብራክህ የተከፈለ ልጅህም የተረገመ ይሆናል ፡ ከምድርህ የተገኘ አዝመራም ይጠፋል ፡ የበጎችህና የላሞችህም መንጋ ርጉም ይሆናል (ይጠፋል) ።

አንተም በመግባትህም በመውጣትህም የተረገምክ ትሆናለህ ። ኢሳ፡ ፴ ፲፯ ፡ ፶፩ ፰ ።

እግዚአብሔርም በንተ ረኃብን ፡ ችጋርን ፡ ቸነፈርን ያመጣብሃል በእጅህ የያዝከውም ሁሉ ይጠፋል ፡ እኔን

ወከ እስከ ይደመስስከ ፍጡነ በበይነ እከየ ምግባሪከ
እስመ ኀደገኒ ።
፳፩ ወያጥሉ እግዚአብሔር ሞተ ላዕሌከ እስከ ያጠፍአከ
ፍጡነ እምድር እንተ ውስቴታ ትበውእ ህየ ከመ ትት
ዋረሳ ።
፳፪ ወይቀሥፈከ እግዚአብሔር በጽዌ ሲሕ ፣ ወበፈጸንት ፣
ወበአስፈር ፣ ወበፍርሃት ፣ ወበድንጋፄ ፣ ወበዐበር ፣ ወበኀ
ጢእ ፣ ወይሰድዱከ እስከ ያጠፍኡከ ።

፳፫ ወትከውን ሰማይ በመልዕልተ ርእስከ ብርተ ፣ ወምድ
ርኒ በታሕቴከ ሐፂነ ።
፳፬ ወይሬስዮ እግዚአብሔር ለዝናመ ምድርከ ቆበረ ፣
ወመሬት ይወርድ እምሰማይ ላዕሌከ እስከ ይቀጠቅጠከ
ወእስከ ያጠፍአከ ።
፳፭ ወይገብረከ እግዚአብሔር ከመ ትትቀተል በቅድመ
ፀርከ በአሐቲ ፍኖት ትወፅእ ኀቤሆሙ ፣ ወበሰቡዑ ፍና
ው ትነትዕ እምቅድመ ገጾሙ ወትከውን ዝርወ ውስተ
ኵሉ መንግሥታተ ምድር ።
፳፮ ወይከውኑ አብድንቲከ መብልዐ ለአዕዋፈ ሰማይ ወኢ
ትረክብ ዘይቀብረከ ።
፳፯ ወይቀሥፈከ እግዚአብሔር በመቅሠፍተ ግብጽ በዐ
በቅ እኩይ ውስተ ነፍስትከ ወበሀከክ ዘአልቦ ፈውስ ።

፳፰ ወይቀሥፈከ እግዚአብሔር በድቀት ወበዓዊር ወበድ
ንጋፄ ልብ ።
፴ ወትገብእ ወታመረስስ መዐልተ ከመ ያመረስስ ዕዉር
በውስተ ጽልመት ወኢትረክብ ፍኖተ ወትትገፋዕ ወትት
በረበር በኵሉ መዋዕሊከ ወኢትረክብ ዘይረድአከ ።
፴ ወታወስብ ብእሲተ ወየሀይደከሃ ካልእ ብእሲ ፣ ወትነ
ድቅ ቤተ ወኢትነብር ውስቴቱ ፣ ወትተክል ወይነ ወኢ
ትቀሥሞ ።
፴፩ ወይጠብሑ ላሕመከ ወኢትበልዕ እምኔሁ ፣ ወየሀይዱ
አድገከ ወኢያገብኡ ለከ ፣ ወይገብኡ አባግዒከ ለአግብርት
ወለፀርከ ወኢትረክብ ዘይረድአከ ።
፴፪ ወይገብኡ ደቂቅከ ወአዋልዲከ ለካልእ ሕዝብ ወት
ሬኢ በአዕይንቲከ እንዘ ይኬርዕዎሙ ወአልቦ ዘትክል
ገቢረ ።
፴፫ ወይበልዕ ሕዝብ ነኪር ዘኢተአምር እክለ ምድርከ
ወጻማከ ፣ ወትከውን ጽዑረ ወሥቁየ በኵሉ መዋዕል ።

፴፬ ወትከውን ምሑዐ በምርአየ አዕይንቲከ ወኢትሬኢ ።

፴፭ ወይቀሥፈከ እግዚአብሔር በደዌ እኩይ ውስተ ብረ
ኪከ ወውስተ አቍያጺከ ወውስተ አዕማደ እገሪከ በዘኢ
ትክል ሐይወ እምሰኰና እግርከ እስከ ርእስከ ።
፴፮ ወይወስደከ እግዚአብሔር ኪያከኒ ወመላእክቲከኒ ዘሤ
ምከ ለከ ውስተ ሕዝብ ዓቢይ ዘኢተአምር አንተ ወኢ
አበዊከ ፣ ወታመልክ በህየ ባዕዳነ አማልክተ ዕፀወ ወአ
እባነ ።

ትተኸኛልና ስለ ሥራህ ክፋት ፈጥኖ እስኪያጠፋህ ድረስ
ሞትን ያጠፋኻል ። ዘዳ፡ ፮ ፳፫ ፣ ሚክ፡ ፪ ፬ ።
ትወርሳት ዘንድ አንተ ከምትገባበት ምድር ፈጥኖ
እስኪያጠፋህ ድረስ እግዚአብሔር ሞትን ያመጣብኻል ።
ዘሌዋ፡ ፳፮ ፲፮ ።
እግዚአብሔርም (በደዌ ሲሕ) በሆድ ደዌና በንዳድ ፣
(አስፈር) በቍርጣት በፍርሃት ፣ በድንጋፄ ፣ በድርቅና እኽ
ልን በማጣት ያጠፋኻል እስኪያጠፋህም ድረስ ከገር
አውጥተው ይሰዱኻል ። ዘሌ፡ ፳፮ ፲፮ ፣ ፩ ነገ፡ ፰ ፴፯ ።
ከራስህ በላይ ያለች ሰማይ ናስ ትሆንብሀለች በበታ
ችህ ያለች ምድርም ብረት ትሆንብሀለች ። ዘሌ፡ ፳፮ ፲፱።
እግዚአብሔርም በምድርህ ላይ የሚዘንመውን ዝናም
ጽጋግ ያደርገዋል ፣ ፈጽሞ እስኪያጠፋህም ድረስ አፈር
(ዋግ) ከሰማይ ይወርድብኻል ።
እግዚአብሔር በጠላትህ ፊት እንድትሞት ያደርግ
ኻል በአንዲት ጐዳና ወደነሳቸው ወጥተህ ከፊታቸው
በሰባት ጐዳና ትሸሻለህ በአሕዛብ መንግሥታትም ሁሉ
ትበተናለህ ። ኤር፡ ፲፭ ፬ ፣ ሕዝ፡ ፳፫ ፵፮ ።
የሚቀብርህ አጥተህ ሬሳዎችህ ለሰማይ ወፎች ምግብ
ይሆናሉ ። ፩ ሳሙ፡ ፲፯ ፵፬ ፣ መዝ፡ ፸፱ ፪ ።
እግዚአብሔር የግብጽ ሰዎችን ባጠፋበት መቅሠ
ፍት በክፉ ችፌ ድኅንነት በሌለበት እከክ ሰውነትህን
ያጠፋኻል ።
እግዚአብሔር በመውደቅ ፣ በዕውርነት (በድንብር
ብር) በልቡናም ድንጋጤ ያጠፋሀል ። ዘዳ፡ ፳፰ ፴፬ ።
ዕውር በጨለማ እንዲርመሰመስ ተመልሰህ በቀን
ትርመሰመሳለህ መንገድም አታገኝም ፣ በዘመንህም ሁሉ
የተገፋህ የተዘረፍህም ትሆናለህ የሚረዳህንም አታገኝም።
ሚስት ታገባለህ ሌላም ሰው ይቀማኻል ፣ ቤትም
ትሠራለህ አትኖርበትም ፣ ወይንን ትተክላለህ ፣ ነገር ግን
ፍሬውን አትለቅምም ። ዘዳ፡ ፳፰ ፮ - ፯ ፣ ፳ ፮ ።
በሬህን ያርዱታል ነገር ግን ከሥጋው አትበላም ፣
አህያህን ይቀሙኻል አይመልሱልህም ፣ በጎችህን ለጠላቶ
ችህና ለባሮችህ አሳልፈው ይሰጣሉ የሚረዳህም አታገኝም።
ወንዶች ልጆችህና ሴቶች ልጆችህ ተማርከው ወደ
አሕዛብ ይሄዳሉ ፣ ራስ ራሳቸውን ሲቀጠቅጧቸው በዓይኖ
ችህ ታያለህ ፣ ነገር ግን ምንም የምታደርገው ነገር የለም።
ከምድርህም የተገኘውን አዝመራህን የደከምክበት
ገንዘብህን የማታውቀው ሕዝብ ይበላብኻል ፣ አንተም በዘ
መንህ ሁሉ የተጨነቅህና የተገፋህ ትሆናለህ ።
ዓይኖችህ በሚያዩት ሁሉ ትሸሻለህ ፣ አታይም (ምሑዐ
ዕብድ ትሆናለህ) ።
ከጫማህ ጀምሮ እስከ ራስህ ድረስ መዳን በማትችል
ገንዘብ እግዚአብሔር ጕልበትህን ጭንህን ባትህን በሚያ
ሳብጥ በክፉ ደዌ ይመታኻል ። ዘዳ፡ ፳፰ ፳፯ ።
እግዚአብሔር በብዙ ሕዝብ ላይ ከሾመልህ አለቆችህ
ጋር አንተ ወደማታውቀው አበቶችህም ወደማያውቁት
አገር አስማርከ ይወስድኻል ፣ በዚያም ሌሎች የዕን
ጨትና የድንጋይ አማልክትን ታመልካለህ ።

፴፰ ወትከውን በህየ ድንጉፀ ፡ ወትከውን አምሳለ ወነገረ ለኵሉ አሕዛብ ዘኀቤሆሙ ይወስደከ እግዚአብሔር ።

በዚያም የደነገጥህ ትሆናለህ ፡ እግዚአብሔር አስማርክ በሚወስድህ በዚያም ለአሕዛብ መተረቻ መዘበቻ ትሆናለህ ። ፩ ነገ፡ ፱ ፯፡ ኤር፡ ፳፬ ፱፡ ሕዝ፡ ፲፬ ፰ ።

፴፱ ወታወፅእ ብዙኀ ዘርአ ውስተ ገራህትከ ወታበውእ ውኁደ እስመ አንበጣ በልዖ ።

በእርሻህ ብዙ ዘር ዘርተህ ጥቂት ታገባለህ ፡ አንበጣ በልቶታልና ። ሚክ፡ ፮ ፲፭፡ ሐጌ፡ ፩ ፮ ።

፵ ወትተክል ዐፀደ ወይን ወትትጌበሮ ወኢትሰቲ እምወይኑ ወኢትትፌሣሕ ቦቱ እስመ ዐፂ እኩይ በልዖ ።

ወይን ተክለህ ትኰተኵተዋለህ ነገር ግን ከወይኑ አትጠጣም ፡ በሱም ደስ አይልህም ክፉ ትል በልቶታልና ።

፵፩ ወታጠሪ ዕፀወ ዘይት ውስተ ኵሉ ደወልከ ወኢትትቀባዕ ቅብዐ እምኔሁ እስመ ተነግፈ ፍሬሁ ።

በአውራጃህ ሁሉ የዘይት ወይራን ትተክላለህ ፡ ነገር ግን ፍሬው ረግፏልና ከሱ ዘይቱን አትቀባም ።

፵፪ ወትወልድ ደቂቀ ወአዋልደ ወኢያተርፍዎሙ ለከ እስመ ይነሥእዎሙ ወይፄውውዎሙ ።

ወንዶች ልጆችንና ሴቶች ልጆችን ትወልዳለህ ፡ ነገር ግን ማርከው ይወስዱዋቸዋል ፡ አያስቀሩልህም ።

፵፫ ወለኵሉ እክለ ምድርከ ወለኵሉ ተክለ ዕፀዊከ አናኵዕ ያጠፍኦ ።

ከምድርህ የተገኘ አዝመራህን አታክልትህንም ሁሉ ኩብኩብ ያጠፋዋል ።

፵፬ ወፈላሲ ዘሀለወ ኀቤከ የዐርግ መልዕልቴከ ወአንተሰ ትከውን መትሕቶ ።

ባንተ ዘንድ ያለ ስደተኛ ካንተ በላይ ይሆናል ፡ አንተም ከሱ በታች ትሆናለህ ። ዘዳ፡ ፳፰ ፲፫ ።

፵፭ ወውእቱ ይሌቅሐከ ወአንተ ኢትሌቅሖ ፡ ውእቱ ይከውነከ ርእሰ ፡ ወአንተ ትከውኖ ዘነበ ።

እሱ ያበድርሃል ፡ አንተ ግን አታበድረውም ፡ እሱ ራስ ይሆንሃል ፡ አንተ ግን ጅራት ትሆነዋለህ ፡ (እሱ ገዥ ይሆንሃል ፡ አንተ ተገዥ ትሆነዋለህ) ። ዘዳ፡ ፳፰ ፲፪ ።

፵፮ ወይመጽእ ላዕሌከ ዝንቱ ኵሉ መርገም ወይዴግነከ ወይረክበከ እስከ ያጠፍእከ ወይደመስሰከ ፡ እስመ ኢሰማዕከ ቃለ እግዚአብሔር አምላክከ ከመ ትዕቀብ ትእዛዞ ወኵነኔሁ ወኵሎ ዘአዘዘከ ።

ይህ ሁሉ ርግማን ይደርስብሃል ፡ ትእዛዙንና ፍርዱን ያዘዘህንም ሁሉ ትጠብቅ ዘንድ የፈጣሪህ የእግዚአብሔርን ቃል አልሰማህምና ፈጽሞ እስኪያጠፋህ ድረስ ይህ ሁሉ መከራ ተከትሎ ያገኝሃል ።

፵፯ ወይኩን ተአምረ ላዕሌከ ወመድምመ ላዕለ ዘርእከ እስከ ለዓለም እስመ ኢያምለክኮ ለእግዚአብሔር አምላክከ በትፍሥሕት ወበሠናይ ልብ ።

ፈጣሪህ እግዚአብሔርን በተድላ በደስታ ፡ በበጎ ልቡና ሁነህ አላመለክኸውምና ባንተ ተአምራት ይደረግብሃል በልጆችህም ለዘለዓለሙ ድንቅ ተአምራት ይደረግባቸዋል ።

፵፰ ወበዝ ኵሉ ትትቀነይ ለጸላእትከ ዘይፌኑ እግዚአብሔር ላዕሌከ በረኃብ ፡ ወበጽምእ ፡ ወበዕርቃን ወበኀጢአ ኵሉ ፡ ወይወዲ ለከ ጋጋ ዘሐፂን ውስተ ክሳድከ እስከ ያጠፍእከ ።

በዚህም ሁሉ ላይ እግዚአብሔር በሚሰድቡህ ጠላቶችህ ትገዛለህ በውኃ ጥምና ፡ በረኃብ ፡ ከልብስ በመራቆትና ሁሉንም በማጣት ትገዛለህ ፡ እስኪያጠፋህም ድረስ በአንገትህ ላይ የብረት ቀንበር (ጽኑ አገዛዝ) ያገባብሃል ።

፵፱ ወያመጽእ እግዚአብሔር ላዕሌከ ሕዝበ እምርሑቅ እምአጽናፈ ምድር ከመ ርደተ ንስር ሕዝበ ዘኢትሰምዕ ነገሮሙ ።

እግዚአብሔር ከአገር ዳርቻ ከሩቅ አገር ቋንቋቸውን የማትሰማው አሕዛብን እንደ አሞራ አወራረድ ፈጥኖ ያመጣብሃል ።

፶ ሕዝበ ግሩመ ገጽ ዘኢያከብር ገጸ ልሂቅ ፡ ወኢይምህር ንኡሰ ።

ፊቱ የሚያስፈራ የሽማግሌን ፊት የማያከብር ፡ ለሕፃንም የማይራራ አሕዛብን ያመጣብሃል ።

፶፩ ወያጠፍእ እጕለ መራዕይከ ወእክለ ምድርከ እስከ ኢያተርፍ ለከ እክለ ፡ ወኢ ወይነ ፡ ወኢ ቅብዐ ፡ ወኢ መራዕየ አልሕምቲከ ወአባግዒከ እስከ ያጠፍእከ ።

ወይንህን ዘይትህን የላሞችህንና የበጎችህን መንጋ ሳያስቀር እስኪያጠፋህ ድረስ ደርሶ ከምድርህ የተገኘውን አዝመራህ ያጠፋብሃል ። ዘዳ፡ ፳፰ ፴፫ ።

፶፪ ወይደመስሰከ እምውስተ ኵሉ አህጉሪከ እስከ ያወድቅ አረፋቲከ ዐበይተ ፡ ወአጽዋኒከ ዘዐቆን ትትአመን ዘውስተ ኵሉ በሐውርቲከ ወይሣቅየከ በውስተ ኵሉ አህጉሪከ ዘወሀበከ እግዚአብሔር አምላክከ ።

በአገርህ ያሉ የምትታመንባቸው አምባዎችህንና የጸኑ ቅጽሮችህን እስኪያፈርሳቸው ድረስ ደርሶ ከአገሮችህ ሁሉ ያጠፋሃል ፡ ፈጣሪህ እግዚአብሔር በሰጠህ አገሮችህ ሁሉ መከራ ያጸናብሃል ። ፪ ነገ፡ ፳፭ ፪ ።

፶፫ ወትገብእ ትብላዕ ውሉደ ከርሥከ ሥጋ ደቂቅከ ወአዋልዲከ ዘወሀበከ እግዚአብሔር አምላክከ በምንዳቤከ ወበሥቃይከ ዘሣቀየከ ጸላኢከ በውስተ አህጉሪከ ።

በአገርህ ሳለህ ጠላትህ በመጣብህ መከራ ሁሉ ፈጣሪህ እግዚአብሔር የሰጠህን ከባሕርይህ የተወለዱ የሴቶች ልጆችህንና የወንዶች ልጆችህን ሥጋ ትበላለህ ።

፶፬ ዘርህጺ ወለምለሚ ወትደነፅ ዐይኑ ለእኁሁ ወለብእሲቱ እንተ ውስተ ኀፅኑ ወለዘተርፉ ውሉድ ዘአትረፉ ሎሙ ።

ባንተ ዘንድ ተድላድሎና ተቀማጥሎ ሁሉ ጊዜ ይኖር የነበረ ሰው ዓይኑ ወንድሙንና አቅፎው የምትተኛ ሚስቱን አሕዛብ ያስቀሩዋቸው ፡ የቀሩ ልጆቹንም ትነፍጋቸዋለህ ። ዘዳ፡ ፲፰ ፱፡ ፲፫ ፯ ።

፶፭ ወይሁብሞሙ ለለአሐዱ እምኔሆሙ ሥጋ ውሉዶሙ ይሴሰዩ ፣ እስመ ኢያተረፉ ሎሙ ወኢምንተኒ በሥቃይ ወበምንዳቤ ዘሣቀዩከ ጸላእትከ በኵሉ አህጉሪከ ።

በአገሮችህ ሁሉ ሳለህ ጠላቶችህ በጾኑብህ መከራ ፣ ምንም ምን አላስቀሩላቸውምና ይመገቡ ዘንድ ከነሳቸው ላንዱም ላንዱም የልጆቻቸውን ሥጋ ይሰጡዋቸዋል ።

፶፮ ወእንተ ርህጽትኒ ይእቲ እምኔክሙ ፣ ወእንተኒ ድክምት ይእቲ ትሜህሮን ለእገሪሃ ሐዊረ ውስተ ምድር እስመ ርኅጽት ይእቲ ወድክምት ወትደነዕም ዐይና ለምታ ዘዲበ ኅፅና ወለወልዳ ወለወለታ ።

ድልድል ቅምጥል ነበረችና ደካማም ናትና ፣ ለእግሮቿ መንገድ ታስተምራቸዋለች ፣ ዓይኗም በጠገቧ የሚተኛ ባሏን ይነፍገዋል ፣ ሴት ልጇቿንና ወንድ ልጇቿንም ይነፍጋቸዋል ። ዘዳ፡ ፳፰ ፶፬ ፣ ኢሳ፡ ፵፯ ፩ ።

፶፯ ወለሥጋሃ ዘእምውስተ አባላ ውእቱ ወሕፃና ዘወለደት ትበልዕ ጽሚተ ስበ ኀጥአት ኵሎ በምንዳቤ ወበሥቃይ ዘይሣቅየከ ጸላኢከ በውስተ አህጉሪከ ።

ከወገኗ የተወለደ ዘመዷንም ዓይኗ ይነፍገዋል ፣ በአገርህ ሳለህ ጠላትህ በጸናብህ መከራ ተይዛ ሁሉን ባጣች ጊዜ በአራስ ቤቷ የወለደችው ልጅዋን በሥውር ትበላዋለች ። ዘፍ፡ ፵፱ ፲ ።

፶፰ ወለእመ ኢሰማዕከ ከመ ትግበር ኵሎ ዘንተ ነገረ ለዝንቱ ሕግ ዘጽሑፍ ውስተ ዝንቱ መጽሐፍ ከመ ትፍራህ ስመ ክቡረ ወስቡሐ ዘእግዚአብሔር አምላክከ ።

በዚህ መጽሐፍ የተጻፈ የዚህን ሕግ ነገር ሁሉ ታደርግ ዘንድ ይህን የከበረና የተመሰገነ የፈጣሪህ የእግዚአብሔርን ስም ትፈራ ዘንድ ባትሰማ ። ዘፀ፡ ፮ ፫ ።

፶፱ ወይገብር እግዚአብሔር ነኪረ መቅሠፍተከ ፣ ወመቅሠፍተ ዘርእከ ፣ ወመቅሠፍተ ዐቢየ ወመድምመ ፣ ወደዌ እኩየ ወሕማመ ።

እግዚአብሔር ያንተንና የልጆችህን መቅሠፍት ልዩ ያደርግብኻል ፣ ታላቅ መቅሠፍትን ክፉ ደዌንና ጽኑ መከራን ያመጣብኻል ። መዝ፡ ፲፯ ፯ ፣ ፴፩ ፳፩ ።

፷ ወይገብእ ላዕሌከ ኵሉ ደዌሆሙ ለግብጽ እኩይ ዝከቱ ዘኢፈራህከ እምኔሁ ወኢፈራህከ እምቅድመ ገጹ ወያተሉ ዲቤከ ።

ከመገለጹ የተነሣ ያልፈራኸው ያ ጽኑ የግብጻውያን መከራ ሁሉ ወዳንተ ይመለሳል ። ዘዳ፡ ፯ ፲፭ ።

፷፩ ወኵሎ ደዌ ወኵሎ መቅሠፍተ ዘኢኮነ ጽሑፈ ውስተ ዝንቱ መጽሐፈ ሕግ ያመጽእ እግዚአብሔር ላዕሌከ እስከ ያጠፍእከ ወእስከ ትደመሰሱ ።

ሕግ በተጻፈበት በዚህ መጽሐፍ ያልተጻፈ ደዌ ሁሉ መቅሠፍቱም ሁሉ ወዳንተ ይመልሳል ፣ እስኪያጠፋህም ድረስ ደርሶ እናንተ ፈጽማችሁ እስክትደመሰሱ ድረስ መከራውን ሁሉ ያመጣባችኋል ።

፷፪ ወትተርፉ ኅዳጣነ በኍልቍ እምድኅረ ኮነ ከመ ከዋክብተ ሰማይ ብዝኅከ እስመ ኢሰማዕከ ቃለ እግዚአብሔር አምላክከ ።

የፈጣሪህ የእግዚአብሔርን ቃል አልሰማህምና ብዛትህ እንደ ሰማይ ከዋክብት ከሆነ በኋላ በቍጥር ጥቂት ትቀራላችሁ ። ዘዳ፡ ፳፯ ፳ ፣ ፲ ፳፪ ።

፷፫ ወበከመ ተፈሥሐ እግዚአብሔር ላዕሌከ ከመ ይግበር ሠናየተ ለከ ወአብዝኅከ ከማሁ ይትፌሣሕ እግዚአብሔር ዲቤከ ከመ ይሥሩከ ወትጠፍእ እምድር እንተ ውስቴታ ትበውእ ህየ ከመ ትትዋረሳ ።

በጎ ነገር ሊያደርግልህ እግዚአብሔር ባንተ ደስ እንዳለው እንዳበዛህም ያጠፋህም ዘንድ እግዚአብሔር ባንተ ጥፋት ደስ ይለዋል ፣ ትወርሳት ዘንድ በዚያ በምትገባበት ምድር ትጠፋለህ ። ኢሳ፡ ፷ ፰ ፣ ኤር፡ ፴፪ ፵፩ ።

፷፬ ወይዘርወከ እግዚአብሔር አምላክከ ውስተ አሕዛብ እምአጽናፈ ምድር እስከ አጽናፈ ምድር ፣ ወትትቀነይ በህየ ለባዕዳን አማልክት ፣ ለዕፀው ወለአእባን ዘኢተአምር አንተ ወኢ አበዊከ ።

ፈጣሪህ እግዚአብሔር ከምድር ዳርቻ ጀምሮ እስከ ምድር ዳርቻ ድረስ በአሕዛብ አገር ይበትንኻል ፣ በዚያም አንተ ለማታውቃቸው አባቶችህም ለማያውቋቸው ለልዩ ልዩ ጣአታት ለደንጊያዎችና ለዕንጨቶች ትገዛለህ ።

፷፭ ወበህየኒ በውስተ ውእቱ አሕዛብ ኢያዐርፈከ ወኢያበውሐከ ትቁም በእግርከ ፣ ወይሁበከ በህየ እግዚአብሔር ልበ ኅዙነ ወአዕይንተ ጥፉአተ ወነፍሰ ሙስንተ ።

በዚያም በአሕዛብ አገር ከመከራ አያሳርፍህም በእግርህም ትቆም ዘንድ አያሳናብትህም ፣ በዚያም እግዚአብሔር ልቡናህን ያሳዝነዋል ፣ ዓይንህን ያፈዘዋል ሰውነትህንም ያደክመዋል ። ዘሌ፡ ፳፮ ፴፯ ፣ አሞ፡ ፱ ፬ ።

፷፮ ወትከውን ሕይወትከ ስቅልተ ቅድመ አዕይንቲከ ወትደነግፅ ለሊከ መዐልተ ወሌሊተ ወኢትትአመን ለሕይወትከ ።

ድኅነትህ ከዓይንህ የራቀች (የተሰቀለች) ትሆናለች ፣ አንተም ቀንም ሌትም ትደነግጣለህ ፣ ሕይወትህንም አታምናትም ።

፷፯ ለእመ ጸብሐ ትብል እፎ እንጋ ይመሲ ፣ ወለእመ መስየ ትብል እፎ እንጋ ይጸብሕ እምፍርሃተ ልብ ዘትደነግፅ ወእምዘያስተርእየከ ውስተ አዕይንቲከ ወዘትሬኢ ።

ሲነጋ እንጃ እንዴት ይመሽል ትላለህ ፣ ሲመሽም ስለ ልብህ ፍርሃት በዓይንህም ከሚታይህ አንተም ከምታየው የተነሣ ሲመሽ እንጃ ፣ እንዴት ይነጋል ትላለህ ።

፷፰ ወያገብአከ እግዚአብሔር ውስተ ግብጽ በአሕማር ወእንተ ምድርኒ በእግር ዝንቱ ዘእቤለከ ኢትደግሙ እንከ ርእዮታ ዳግመ ።

እግዚአብሔርም በባሕር በመርከብ በየብስም በእግር ወደ ግብጽ ይመልስኻል ፣ ዳግመኛ አታያትም ያልኩህ ይህ ነው ። ኤር፡ ፵፫ ፯ ፣ ሆሴዕ ፰ ፲፫ ።

፷፰ ወትከውኑ በህየ አግብርተ ወአእማተ ለፀርክሙ ወአልቦ ዘይምሕረክሙ ።

## ምዕራፍ ፳፱ ።

፩ ወዝንቱ ውእቱ ነገረ ኪዳን ዘአዘዘ እግዚአብሔር ለሙሴ ከመ ይትከየዶሙ ለደቂቀ እስራኤል በምድረ ሞአብ ዘእንበለ ዝክቱ ኪዳን ዘተከየዶሙ በኮሬብ ።

፪ ወጸውዖሙ ሙሴ ለኵሉ ደቂቀ እስራኤል ወይቤሎሙ ለሊክሙ ርኢክሙ ኵሎ ዘገብረ ለክሙ እግዚአብሔር በምድረ ግብጽ ላዕለ ፈርዖን ወላዕለ መገብቱ ወላዕለ ኵሉ ዓበይቱ ወላዕለ ኵሉ ምድሩ ።

፫ መቅሠፍተ ዓቢየ ዘርእያ አዕይንቲክሙ ወዝክተ ተአምረ ፡ ወመድምመ ዐቢየ ፡ ወእደ ጽንዕተ ፡ ወመዝራዕተ ልዑለ ።

፬ ወወሀበክሙ እግዚአብሔር አምላክክሙ ልበ ከመ ታእምሩ ፡ ወዐይነ ከመ ትርአዩ ፡ ወዕዝነ ከመ ትስምዑ ፡ እስከ ዛቲ ዕለት ።

፭ ወወሰደክሙ አርብዓ ዓመተ ውስተ ገዳም ፡ ወአልባሲክሙኒ ኢበልየ ወአሣእኒክሙኒ ኢበልየ እምእገሪክሙ ።

፮ እንዘ እክለ ኢትበልዑ ፡ ወወይነ ወሜሰ ኢትሰትዩ እስከ በጻሕክሙ ውስተ ዝንቱ መካን ከመ ታእምሩ ከመ ውእቱ እግዚአብሔር አምላክክሙ ።

፯ ወወፅአ ሴዎን ንጉሠ አሞሬዎን ወዖግ ንጉሠ ባሳን ፡ ወተቀበሉክሙ ይትቃተሉክሙ ወቀተልናሆሙ ወነሣእነ ምድሮሙ ።

፰ ወወሀብክዎሙ ይእተ ምድረ ለሮቤል ወለጋድ ወለመንፈቀ ነገደ ምናሴ ።

፱ ወዕቀቡ ከመ ትግበሩ ኵሎ ነገረ ዝንቱ ኪዳን ከመ ታእምሩ ኵሎ ዘትገብሩ ።

፲ ወናሁ ቆምክሙ አንትሙ ኵልክሙ ቅድመ እግዚአብሔር አምላክክሙ ፡ ወዐበይተ ነገድክሙ ፡ ወሊቃውንቲክሙ ፡ ወመኳንንቲክሙ ወጸሐፍቲክሙ ፡ ወኵሉ ተባዕተ እስራኤል ።

፲፩ ወአንስትያክሙ ፤ ወውሉድክሙ ወግዩር ዘሀለወ ማእከለ ትዕይንቲክሙ እምሐጣቤ ዕፀክሙ እስከ ሐዋሬ ማይክሙ ።

፲፪ ከመ ትስምዑ ኪዳኖ ለእግዚአብሔር አምላክክሙ ወመርገሞኒ ለእግዚአብሔር አምላክክሙ ዘተከየደ ምስሌክሙ ዮም ።

፲፫ ከመ ይረሲከ ሕዝበ ሎቱ ፡ ወውእቱኒ ከመ ይኩንከ አምላከ ፡ በከመ መሐለ ለአበዊከ ለአብርሃም ወለይስሐቅ ወለያዕቆብ ።

፲፬ ወአኮ ለክሙ ለባሕቲትክሙ ዘአቀውም አነ ዘንተ ኪዳነ ወዘንተ መርገመ ።

፲፭ አላ ለእለሂ ሀለዉ ዝየ ዮም ምስሌክሙ ቅድመ እግዚአብሔር አምላክክሙ ፡ ወለእለሂ ኢሀለዉ ዝየ ምስሌክሙ ዮም ።

በዚያም ለጠላቶቻችሁ ሴቶች ባሮችና ወንዶች ባሮች ትሆናላችሁ ይቅር የሚላችሁም የለም ።

## ምዕራፍ ፳፱ ።

በኮሬብ ከተማማላቸው ከዚህ ቃል ኪዳን ነገር በቀር የእስራኤልን ልጆች በሞአብ አውራጃ ይማማላቸው ዘንድ እግዚአብሔር ለሙሴ ያዘዘው የቃል ኪዳን ነገር ይህ ነው ።

ሙሴም የእስራኤልን ልጆች ሁሉ ጠርቶ ፈጣሪያችሁ እግዚአብሔር በፈርዖንና በሹማምንቱ በመኳንንቱም በአገሩም ሁሉ በግብጽ አገር ያደረገላችሁን ሁሉ እናንተ አይታችኋል አላቸው ። ዘፀ፡ ፲፱ ፬ ፡ ዘዳ፡ ፳ ፫ ።

ዓይኖቻችሁ ያዩትን መቅሠፍትን ያነንም የተደነቀና ገናና ተአምራት የጸናች እጅንና የተዘረጋች ክንድን አይታችኋል ።

ፈጣሪያችሁ እግዚአብሔርም ታውቁ ዘንድ ልብን ፡ ታዩ ዘንድ ዓይንን ትሰሙ ዘንድ ጆሮን እስከዚች ቀን ድ ስ ሰጣችሁ ። ኢሳ፡ ፮ ፱ ፡ ዮሐ፡ ፳ ፵፫ ።

እግዚአብሔር በምድረ በዳ አርባ ዘመን አዘራችሁ ፡ ልብሳችሁ አላለቀም ፡ በእግራችሁ ያለ ጫማችሁም አላረጀም ። ዘዳ፡ ፩ ፫ ፡ ፳ ፬ ።

እሱ እግዚአብሔር ፈጣሪያችሁ እንደሆነ ታውቁ ዘንድ እኽል ሳትበሉ ፡ ወይንንና ጠጅን ሳትጠጡ ፡ እስከዚህ ቦታ ድረስ ደረሳችሁ ። ዘፀ፡ ፲፯ ፬ ፡ ዘዳ፡ ፳ ፫ ።

የባሳን ንጉሥ ዓግና የሐሴቦን ንጉሥ ሴዎን ወጥተው ይዋጉን ዘንድ ተቀበሏችሁ ፡ ወጋናቸው አገራቸውንም ወሰድን ። ዘዳ፡ ፪ ፴፪ ፡ ፫ ፩ ።

ያችንም አገር ለሮቤልና ለጋድ ለምናሴ ነገድ እኩሌታም ሰጠኋቸው ። ዘዳ፡ ፫ ፲፫ ፡ ዘኍ፡ ፴፪ ፴፫ ።

የምታደርጉትን ሁሉ ታውቁ ዘንድ የዚህን የቃል ኪዳን ነገርም ታደርጉ ዘንድ ሕጉን ፡ ጠብቁ ።

እናንተም ሁላችሁ በፈጣሪያችሁ በእግዚአብሔር ፊት እነሆ ቆማችኋል ፡ የነገዶቻችሁ ሹማምሮች ፡ አለቆቻችሁ መኳንንቶቻችሁና ጸሐፊዎቻችሁ ፡ የእስራኤልም ወንዶች ሁሉ ።

ሚስቶቻችሁ ልጆቻችሁ በከተማችሁ ያለ ስደተኛ ፡ ዕንጨት ለቃሚያችሁና ፡ ውኃ ቀጂያችሁ ሁሉ ።

አሁን ከናንተ ጋር የተማማለው የእግዚአብሔር መርገሙንና የፈጣሪያችሁ የእግዚአብሔርን ቃል ኪዳኑን ትሰሙ ዘንድ ።

ለአባቶቻችሁ ለአብርሃም ፡ ለይስሐቅና ለያዕቆብ እንደ ማለላቸው እርሱ ላንተ የፍቅር አባት ትሆነው ዘንድ አንተም ለሱ ወገን ትሆነው ዘንድ እነሆ በፊቱ ቆማችኋል ።

እኔም ይህን ቃል ኪዳንና ይህን ርግማን በናንተ ላይ ብቻ የማጸናው አይደለም ። ዘፍ፡ ፲፰ ፯ ፡ ዘፀ፡ ፯ ፯ ።

አሁን በዚህ ከናንተ ጋራ በፈጣሪያችሁ በእግዚአብሔር ፊት ለሌሉና አሁን በዚህ ከናንተ ጋራ ላሉም ነው እንጂ ። ግብ፡ ሐዋ፡ ፪ ፴፱ ።

፲፮ እስመ ለሊክሙ ተአምሩ ዘከመ ነበርነ ውስተ ግብጽ ፣ ወዘከመ ኀለፍነ እንተ ማእከሎሙ ለአልክቱ አሕዛብ ወተ ዐደውናሆሙ ።

በግብጽ እንደ ኖርን በነዚህም አሕዛብ መካከል አል ፈናቸው እንደ ሄድን እናንተ ታውቃላችሁና ።

፲፯ ወርኢክሙ ርኵሶሙ ወአማልክቲሆሙ ዕፀ ፣ ወእብነ ፣ ወብሩረ ፣ ወወርቀ ወብርተ ፣ ዘገብሩ ለሊሆሙ ።

እነሱ የሠሩዋቸው ደንጊያንና ዕንጨትን ፣ ወርቅንና ብርን ናስንም የሚሆኑ ጣኦቶቻቸውንና ኃጢአታቸውን አይታችኋል ። ዘሌ፡ ፳፮ ፴ ፣ ፩ ነገ፡ ፳፩ ፳፮ ።

፲፰ ኢይኩን እምኔክሙ ኢ ብእሲ ወኢ ብእሲት ፣ ወኢ ሕዝብ ፣ ወኢ ነገድ ፣ ወኢ መኑሂ ዘያኀድግ ልበ እምእግዚ አብሔር አምላክክሙ ፣ ወየሐውር ያምልክሙ ለእልክቱ አማልክተ አሕዛብ ወኢይኩን እምኔክሙ ሥርው እኪት እንተ ታበቍል ወታፈሪ ሐምዘ ወምረተ ።

ወንድም ቢሆን ሴትም ብትሆን ወገንም ቢሆን ፣ ነገ ድም ቢሆን ፣ ማንም ማን ልቡናውን ከፈጣሪያችሁ ከእግ ዚአብሔር አርቆ እነዚያን የአሕዛብ ጣኦቶች የሚያመልክ ቸው ከናንተ አይገኝ ፣ ከናንተም ሐሞትንና እሬትን የሚ ያበቅል ክፉ ሥር (ልቡና) አይኑርባችሁ ።

፲፱ ወሰሚዐክሙ ቃለ ዝንቱ መርገም ዘያቤ በልቡ ይሠሬ ኢት እስመ በዕበየ ልብየ ገበርኩ ወሖርኩ ከመ ኢያዐሪ መዊተ መአብስ ምስለ ዘኢአበሰ ።

የዚህን የርግማን ነገር ከሰማችሁ በኋላ ሂጄ በልቡ ናዬ ስንፍና አድርጌዋለሁና በልቡ እግዚአብሔር ይቅር ይለኛል የሚል ሰው ቢኖር አውቆ የበደለ ሰው ሳያውቅ ከበደለ ሰው ጋራ በፍዳ እንዳይተካከል ይወቅ ።

፳ ኢይፈቅድ እግዚአብሔር ከመ ይሣሀሉ አላ በጊዜሃ መዐቱ ለእግዚአብሔር ፣ ወቅንኡ ያውዕዮ ለውእቱ ብእ ሲ ፣ ወይተልዎ ዝንቱ ኵሉ መርገም ዘዝንቱ ኪዳን ዘጽ ሑፍ ውስተ ዝንቱ መጽሐፈ ሕግ ወይስዕር እግዚአብሔር ስሞ እምታሕተ ሰማይ ።

የእግዚአብሔር ቍጣውና ለአምላክነቱ የቀናው ቅናት ፈጥኖ ያጠፋዋል እንጂ በዚህም በዳግም ሕግ የተጻፈ የዚ ህ የቃል ኪዳን ርግማን ይከተለዋል እንጂ እግዚአብሔርም ከሰማይ በታች ስሙን ያጠፋል እንጂ ይቅር ይለው ዘንድ አይወድም ። መዝ፡ ፸፱ ፭ ፣ ፸፱ ፳ ።

፳፩ ወያግብኦ እግዚአብሔር ውስተ እኪት ወይፍልጦ እም ኵሉ ደቂቀ እስራኤል በኵሉ ዝንቱ መርገም ዘዝንቱ ኪ ዳን ዘጽሑፍ ውስተ ዝንቱ መጽሐፈ ሕግ ።

በዳግም ሕግ በተጻፈ በዚህ በመሐላው መርገም ሁሉ ከእስራኤል ልጆች ሁሉ ለይቶ ፣ እግዚአብሔር በመከራ ይጥለዋል ። ዘዳ፡ ፴ ፲ ።

፳፪ ወይብሉ ድኅረ ትውልድ ደቂቅክሙ እለ ይትነሥኡ እምድኅሬክሙ ወነኪርኒ ዘይመጽእ እምርኁቅ ብሔር ወይሬእዩ መቅሠፍታ ለይእቲ ምድር ወደዌሃ ዘፈነወ እግ ግዚአብሔር ላዕሌሃ ።

ከናንተ በኋላ የሚነሱ ልጆቻችሁና ከሩቅ አገር የሚ መጣ ባዕድም እግዚአብሔር ያመጣበት የዚያችን አገር መከራዋ መቅሠፍቷን ያያሉ ። ዘዳ፡ ፳፬ ፳፬ ።

፳፫ ተይ ፣ ወጼው ፣ ይነድድ ውስተ ኵለንታሃ ፣ ወኢትዘ ራእ ፣ ወኢታበቍል ወኢይወዕእ ውስቴታ ኵሉ ሐመል ማል በከመ ተገፍትዓ ሰዶም ፣ ወገሞራ ፣ ወአዳማ ፣ ወሴባ ዮን ፣ እለ ገፍትዖን እግዚአብሔር በመዐቱ ።

በሁለንተናዋ ድኝ ፣ ጨው (እሳት) ሲነድ ዘር ሳይዘራ ባት ቡቃያን ሳታበቅል እግዚአብሔር ተቈጥቶ ያጠፋቸው ገሞራና ሰዶም ሴባዮና አዳማ እንደጠፉ በቧም ልምላሜ ሳታወጣና ሳታስገኝ አይተው ። መሳ፡ ፱ ፵፭ ።

፳፬ ወይብሉ ኵሉ አሕዛብ ለምንት ከመዝ ገብራ እግዚአ ብሔር ለዛቲ ምድር ፣ ወምንት ውእቱ መንሱቱ ለዝንቱ መዐት ዐቢይ ።

አሕዛብ ሁሉ እግዚአብሔር ይህችን አገር ለምን እን ዲህ አደረጋት ፣ የዚህስ የጽኑ መዓት ጥፋት ምንድር ነው ፣ ይላሉ ። ዘዳ፡ ፳፬ ፳፬ ።

፳፭ ወይብሉ እስመ ኀደጉ ኪዳኖ ለእግዚአብሔር አምላከ አበዊሆሙ ዘተካየደ ምስለ አበዊሆሙ አመ አውፅኦሙ እምድረ ግብጽ ።

መለሾችም ከግብጽ አገር በወጣቸው ጊዜ ከአባቶቻ ቸው ጋር የተማማለውን ያባቶቻቸውን ፈጣሪ የእግዚአብ ሔርን ቃል ኪዳን አፍርሰዋልና ።

፳፮ ወሖሩ ወአምለኩ ባዕዳነ አማልክተ ወሰገዱ ሎሙ ለዘኢየአምሩ ወለዘኢይበቍዕዎሙ ።

ሂደውም ልዩ የሆኑ ጣኦታትን አምልከዋልና ለማያ ውቋቸውና ለማይጠቅሟቸውም ሰግደውላቸዋልና ።

፳፯ ወተምዐ መዐተ እግዚአብሔር ላዕለ ዛቲ ምድር ወአ ምጽአ ላዕሌሃ ኵሎ መርገመ ዘጽሑፍ ውስተ ዝንቱ መጽ ሐፈ ሕግ ።

እግዚአብሔር በዚህች አገር ላይ ፈርዶ (ተቈጥቶ) በዚህ በዳግም ሕግ የተጻፈውን ርግማን ሁሉ አመጣበት ። መዝ፡ ፲፩ ፮ ።

፳፰ ወአስዐሮሙ እግዚአብሔር እምገጸ ምድሮሙ በመ ዐት ወበመንሱት ወበመቅሠፍት ዐቢይ ከመ ይእዜ ዘን ቡእ ለእግዚአብሔር አምላክነ ።

እግዚአብሔር ከአገራቸው በጥፋት በጽኑ መቅሠፍት በቍጣ አጠፋቸው ፣ ዛሬ እኛ እንደምንቀበለው ያለ መቅ ሠፍት ለፈጣሪያችን ለእግዚአብሔር የተሠወረ መቅሠፍት አለው ።

፳፱ ወዘኢያስተርኢ ለነ ወለውሉድነ ለዓለም ከመ ንግ በር ኵሉ ዘይብል ዝንቱ ሕግ ።

የሚታየው (የተገለጸው) መቅሠፍት ግን ይህ ዳግም ሕግ የሚያዘውን ሁሉ እናደርግ ዘንድ ፣ ለኛና ለዘለዓ ለምም ለልጆቻችን ነው ፣ ብለው ይመልሱላቸዋል ።

## ምዕራፍ ፴ ።

፩ ወእመ መጽአ ላዕሌከ ኵሉ ዝንቱ ነገር በረከቱሂ ወመርገሙሂ ዘአቀምኩ ቅድሜከ ተዘከር በልብከ በውስተ ኵሉ አሕዛብ ኀበ ዘረወከ እግዚአብሔር ህየ ።

፪ ወተመየጥ ኀበ እግዚአብሔር አምላክከ ወስማዕ ቃሎ ኵሎ ዘአነ እኤዝዘከ ዮም በኵሉ ልብከ ወበኵሉ ነፍስከ ።

፫ ወየኀድግ ለከ እግዚአብሔር ኵሎ ኃጢአቲከ ወይሣሃለከ ወከዐበ ያስተጋብአከ እግዚአብሔር እምኵሉ አሕዛብ እለ ውስቴቶሙ ዘረወከ ህየ ።

፬ ወለእመኒ ውስተ አጽናፈ ሰማይ ዘረወከ ያስተጋብአከ እምህየ እግዚአብሔር አምላክከ ።

፭ ወይወስደከ ውስተ ይእቲ ምድር እንተ ተወረሱ አበዊከ ወትወርሳ ወይገብር ሠናይተ ላዕሌከ ወያበዝኃከ ወይፌድየከ ፈድፋደ እምአበዊከ ።

፮ ወያሴስሎ እግዚአብሔር ለዝክቱ ልብከ ወልቦሙ ለዘርእከ ከመ ታፍቅሮ በኵሉ ልብከ ፡ ወበኵሉ ነፍስከ ከመ ትሕየው አንተ ወዘርእከ ።

፯ ወያገብእ እግዚአብሔር አምላክከ ለዝንቱ መርገም ላዕለ ፀርከ ወላዕለ እለ ይጸልኡከ ፡ ወላዕለ እለ ይሰድዱከ ።

፰ ወአንተሰ ተመየጥ ወስማዕ ቃለ እግዚአብሔር አምላክከ ወግበር ኵሎ ትእዛዞ ዘአነ እኤዝዘከ ዮም ።

፱ ወብዙኀ ያጸንዐከ እግዚአብሔር አምላክከ በኵሉ ተግባረ እደዊከ ወበውሉደ ከርሥከ ወበዘርአ ምድርከ ፡ ወበ አስተዋልዶ እንስሳከ ፡ እስመ ይትመየጥ እግዚአብሔር አምላክከ ከመ ይትፈሣሕ ላዕሌከ በሠናይ በከመ ተፈሥሐ ላዕሌከ በእኩይ ወበከመ ተፈሥሐ ላዕለ አበዊከ ።

፲ ለእመ ሰማዕከ ቃለ እግዚአብሔር አምላክከ ከመ ትዕቀብ ወከመ ትግበር ኵሎ ትእዛዞ ወኵሎ ኵነኔሁ ወፍትሖ ዘጽሑፍ ውስተ ዝንቱ መጽሐፈ ሕግ ወለእመ ገባእከ ኀበ እግዚአብሔር አምላክከ በኵሉ ልብከ ወበኵሉ ነፍስከ ።

፲፩ እስመ ዛቲ ትእዛዝ ዘአነ እኤዝዘከ ዮም ኢኮነት ክብደ ወኢኮነት ርኅቅተ እምኔከ ።

፲፪ ወኢኮነት ውስተ ሰማይ ከመ ኢትበል መኑ የዐርግ ውስተ ሰማይ ወያመጽኣ ለነ ወንሰምዓ ወንግበራ ።

፲፫ ወኢኮነት ማዕዶተ ባሕር ወእመ ትብል መኑ እምዐደወ ለነ ማዕዶተ ባሕር ወያመጽኣ ለነ ወያሰምዓነሃ ወንግበራ ።

፲፬ እስመ ናሁ ቅርብት ይእቲ ለከ ጥቀ ቃል ውስተ አፉከ ወውስተ ልብከ ወውስተ እደዊከ ከመ ትግበራ ።

፲፭ ወናሁ ሜምኩ ቅድመ ገጽከ ዮም ሕይወተ ፡ ወሞተ ፡ ሠናይተ ፡ ወእኪተ ።

፲፮ ወሕይወትሰ ለእመ ሰማዕከ ቃለ እግዚአብሔር አምላክከ ወዐቀብከ ትእዛዘ ኵሎ ዘአነ እኤዝዘከ ዮም ፡ ከመ

## ምዕራፍ ፴ ።

፩ ይህ ሁሉ ነገር በመጣብህ ጊዜ በፊትህ ያኖርሁት ርግማኑና ምርቃቱ በደረሰብህ ጊዜ እግዚአብሔር በሚበትንህ በዚያ በአሕዛብ አገር ሁሉ በልብህ አስበው ።

፪ እኔ አሁን የማዝህን ቃሉን ሰምተህ በፍጹም ሰውነትህ ፡ በፍጹም ልቡናህ ወደ ፈጣሪህ ወደ እግዚአብሔር ተመለስ ። ኢሳ ፶፭ ፯ ፡ ኤር ፡ ፫ ፳ ።

፫ እግዚአብሔርም ይቅር ብሎ ኃጢአትህን ያስተሠርይልሃል ፡ ዳግመኛም እግዚአብሔር በነሳቸው ዘንድ ከበተነህ ከዚያ ከአሕዛብ ሁሉ ይሰበስብሃል ።

፬ በሰማይ ዳርቻም ቢበትንህ ፈጣሪህ እግዚአብሔር ከዚያ ይሰበስብሃል ። ዘዳ፡ ፳፰ ፷፬ ፡ ነህ፡ ፩ ፱ ።

፭ አባቶችህ ወደ ወረሱዋት ወደዚያችም አገር ይመልስሃል ፡ ትወርሳትም አለህ ፡ በጎ ነገርንም ያደርግልሃል ከአባቶችህ ይልቅ ፈጽሞ እንድትበዛ ያደርግሃል ።

፮ እግዚአብሔርም ይህን አላዋቂ ልብህንና የልጆችህን ልብ አንተም ልጆችህም በሕይወት እንድትኖሩ በፍጹም ልቡናህ ፡ በፍጹም ሰውነትህ እንድትወደው ያደርግሃል ።

፯ ፈጣሪህ እግዚአብሔር ይህን ርግማኑን ወደ ተጸራሪዎችህና ከገር አስወጥተው ወደ ሚሰዱህ ጠላቶችህ ይመልሰዋል ።

፰ አንተ ግን ተመልሰህ የፈጣሪህ የእግዚአብሔርን ቃል ስማ ፡ እኔ አሁን የማዝህንም ትእዛዙን ሁሉ አድርግ ።

፱ ፈጣሪህ እግዚአብሔርም በእጅህ ሥራ ሁሉ ከባሕርይህ በተከፈለው ልጅህና ከምድርህ በሚገኘው አዝመራ ከብቶችህንም በማዋለድ (በማራባት) እጅግ ያጸናሃል ፡ በንተም ጥፋት በአባቶችህም ጥፋት ደስ እንዳለው በንተም ድኅነት ደስ ይለው ዘንድ በረድኤት ወዳንተ ይመለሳልና ።

፲ በዚህ በዳግም ሕግ የተጻፉት ትእዛዙን ቅጣቱንና ፍርዱን ሁሉ ትጠብቅና ትሠራውም ዘንድ የፈጣሪህ የእግዚአብሔርን ቃል ብትሰማ በፍጹም ልቡናህና በፍጹም ሰውነትህም ወደ ፈጣሪህ ወደ እግዚአብሔር ብትመለስ ወዳንተ ይመለሳልና ። ዘዳ፡ ፳፩ ፲፩ ፡ ፳፰ ፷፫ ።

፲፩ እኔ አሁን የማዝህ ይህች ትእዛዝ የከበደች የጸናች አይደለችም ከንተም የራቀች አይደለችም ።

፲፪ ሰምተን እንሠራት ዘንድ ወደ ሰማይ ወጥቶ ማን ያመጣልናል እንዳትል በሰማይም አይደለችም ።

፲፫ ሰምተን እናደርጋት ዘንድ ወንዙን ተሻግሮ አምጥቶ ማን ባሰማን ነበር ብትልም ከባሕር ማዶ አይደለችም ። ምሳ፡ ፴ ፬ ፡ ዮሐ፡ ፫ ፲፫ ፡ ሮሜ ፲ ፮ ።

፲፬ በፍህ ልታስተምራት ፡ በልብህ ልትጠብቃት ፡ በእጅህም ልትሠራት ፡ እነሆ ይህች ቃል ላንተ እጅግ ቅርብ ናት ።

፲፭ ሞትንና ሕይወትን ፡ ክፉንና በጎንም ፡ እነሆ በፊትህ አኖርኩልህ ። ዝዳ፡ ፴ ፲፱ ፡ ሮሜ ፲፮ ፯ ።

፲፮ ሕይወት ፈጣሪህ እግዚአብሔርን ትወደው ዘንድ እኔ አሁን የማዝህን ትእዛዙን ሁሉ ትጠብቅ ዘንድ በሕጉም

ታፍቅር ለእግዚአብሔር አምላክከ ወትሑር በኵሉ ፍና
ዊሁ ፡ ወትዕቀብ ኵነኔሁ ወፍትሖ ወትትበዛኅ ወተሐዩ ወይ
ባርከከ እግዚአብሔር አምላክከ በኵሉ ምድር እንተ ውስ
ቴታ ትበውእ ህየ ከመ ትትዋረሳ ።

፲፯ ወለእመሰ ተመይጠ ልብከ ወአበይከ ሰሚዐ ወስሕትከ
ወሰገድከ ለባዕዳን አማልክት ወተቀነይከሙ ፡ ናሁ አይዳዕ
ኩከ ዮም ከመ ጠፊአ ትጠፍእ ።
፲፰ ወኢይነውኅ መዋዕሊከ ውስተ ምድር እንተ ውስቴታ
ዓዲወ ተዓዱ ዮርዳኖስ ህየ ከመ ትትዋረሳ ።
፲፱ ወናሁ አሰምዕ ለከ ዮም ሰማየ ወምድረ ከመ ሜምኩ
ቅድሜከ ሕይወተ ወሞተ ፡ በረከተ ወመርገመ ፡ ወኅረያ
ለከ ለሕይወት ከመ ትሕየው አንተ ወዘርእከ ።

፳ ወአፍቅሮ/ ለእግዚአብሔር አምላክከ ወሰማዐ ቃሎ
ወአጽንዖ ኪያሁ እስመ ውእቱ ሕይወትከ በዘበቱ ይነውኅ
መዋዕሊከ ከመ ትንበር ውስተ ምድር ዘመሐለ እግዚአብ
ሔር ለአበዊከ ለአብርሃም ወለይስሐቅ ወለያዕቆብ ከመ
የሀበሙ ።

ምዕራፍ ፴፩ ።

፩ ወፈጸመ ሙሴ ተናግሮቶሙ ለኵሉ ደቂቀ እስራኤል
ዘንተ ኵሎ ነገረ ።
፪ ወይቤሎሙ ምእት ወዕሥራ ዓመት ሊተ ዮም ፡ ወኢ
ክል እንከ በዊአ ወወፂአ፡ ወበሕቱ ይቤለኒ እግዚአብሔር
ኢተዐድዎ ለዝንቱ ዮርዳኖስ ።
፫ ወውእቱ እግዚአብሔር ዘየሐውር ቅድሜከ ያጠፍ
ኦሙ እምቅድመ ገጽከ ለኵሉ አሕዛብ፡ ወኢያሱኒ የሐ
ውር ቅድመ ገጽከ በከመ ይቤ እግዚአብሔር ።
፬ ከማሁ ይገብሮሙ በከመ ገብሮሙ ለሴዎን ወለዓግ
ክልኤቱ ነገሥተ አሞሬዎን እለ ይነብሩ ውስተ ማዕዶተ
ዮርዳኖስ ወለምድሮሙ በከመ ሠረዎሙ ።

፭ ወአግብአሙ እግዚአብሔር ለክሙ ወግበርዎሙ በከ
መ አዘዝኩክሙ ።
፮ ትበዐ ወጽናዕ ወኢትፍራህ ወኢትደንግፅ ወኢትዕብስ
በቅድመ ገጾሙ እስመ እግዚአብሔር አምላክከ ውእቱ
የሐውር ምስሌከ ወኢየኀድገከ ወኢያሰትተከ ።
፯ ወጸውዖ ሙሴ ለኢያሱ ወይቤሎ በቅድመ ኵሉ እስ
ራኤል ትበዐ ወጽናዕ እስመ አንተ ትበውእ ቅድሜሁ ለዝ
ንቱ ሕዝብ ውስተ ምድር ዘመሐለ እግዚአብሔር ለአበዊ
ክሙ ከመ የሀበሙ ወአንተ ታወርሰሙ ።
፰ ወእግዚአብሔር የሐውር ምስሌከ ወኢየኀድገከ ወኢ
ያሰትተከ ወኢትፍፍራህ ወኢትደንግፅ ።
፱ ወጸሐፎ ሙሴ ለዝንቱ ነገረ ሕግ ውስተ መጽሐፍ ወወ
ሀበሙ ለካህናት እለ ይፀውሩ ታቦተ ሕጉ ለእግዚአብሔር
ለደቂቀ ሌዊ ወለሊቃውንቲሆሙ ለደቂቀ እስራኤል ።

ጸንተህ ትኖር ዘንድ ፍርዱንና ሥርዓቱን ትጠብቅ ዘንድ
የፈጣሪህ የእግዚአብሔርን ቃል ብትሰማ ነው ፡ ይህን ሁሉ
ብታደርግ ትበዛለህ በሕይወትም ትኖራለህ ፡ ትወርሳት
ዘንድ በምትገባበትም አገር ሁሉ በዚያ እግዚአብሔር
ያከብርኻል ፡ (ይባርከኻል) ። ዘዳ፡ ፯ ፳ ፡ ፩ ፲፱ ።
ልቡናህ ወደ ኃጢአት ቢመለስ መስማትንም እምቢ
ብትል ከሕጉም ወጥተህ ብትስት ልዩ ለሆኑ አማልክትም
ብትሰግድ ግን ፡ ፈጽመህ እንድትጠፋ እኔ አሁን ነገርኩህ።
ትወርሳትም ዘንድ ወደዚያ ዮርዳኖስን በምትሻገርበት
ምድርም ዘመንህ (ዕድሜህ) አይበዛም ። ዘዳ፡ ፳፯ ፫ ።
ሞትንና ሕይወትን ፡ ርግማንና ምርቃትን ፡ በፊትህ አን
ዳኖርኩልህ እነሆ እኔ አሁን ሰማይንና ምድርን አስማብኻ
ለሁ ፡ አንተ ከልጆችህ ጋር በሕይወት ትኖር ዘንድ ሕይ
ወትን ምረጣት ። ዘዳ፡ ፴፬ ፵ ።
ፈጣሪህ እግዚአብሔርን ውደደው ፡ ቃሉንም ስማ ፡
ይሰጣቸው ዘንድ ለአባቶችህ ለአብርሃም ፡ ለይስሐቅና
ለያዕቆብ እግዚአብሔር በማለላቸው ምድር ጸንተህ እንድ
ትኖር ፡ ዘመንህ በሚበዛ ገንዘብ እሱ ሕይወትህ ነውና
እሱን አጽናው ። ዘዳ፡ ፲ ፳ ፡ መዝ፡ ፳፯ ፩ ።

ምዕራፍ ፴፩ ።

ሙሴ ይህን ሁሉ ነገር ለእስራኤል ልጆች ሁሉ ተና
ግሮ ጨረሰ ።
አሁን እኔ መቶ ሃያ ዘመን ሁኖኛል ፡ መውጣትና መግ
ባት አችላለሁ ፡ ነገር ግን እግዚአብሔር ይህን ዮርዳኖስ
አትሻገረውም አለኝ አላቸው ። ዘኍ፡ ፳፯ ፲፯ ።
ፊታውራሪ ሁኖ በፊትህ የሚሄድ እግዚአብሔር አሕ
ዛብን ሁሉ ከፊትህ ያጠፋቸዋል ፡ በፊትህ የሚሄድ ኢያ
ሱም እግዚአብሔር እንዳለ ያጠፋቸዋል ።
በዮርዳኖስ ማዶ የሚኖሩ ሁለቱን የአሞሬዎን ነገሥ
ታት ዓግንና ሴዎንን እንዳጠፋቸው እንዲሁ ያጠፋቸዋል ፡
አገራቸውንም እንዳጠፋባቸው አገራቸውንም ያጠፋ
ባቸዋል ። ዘኍ፡ ፳፩ ፳፫ ፡ ዘዳ፡ ፫ ፳፩ ።
እግዚአብሔር በእጃችሁ ጥሎላችኋል እንዳዘዝኳች
ሁም አድርጓቸው አላቸው ። ዘዳ፡ ፯ ፪ ።
ጨክን በርታ ፡ አትፍራ ፡ አትደንግጥ እሱ እግዚአብ
ሔር በረድኤት ካንተ ጋራ ይኖራልና ፡ አይለይህምና አያ
ቃልልህምና በፊታቸው አትድከም ።
ሙሴም ኢያሱን ጠርቶ ይሰጣቸው ዘንድ እግዚአብ
ሔር ላባቶቻችሁ ወደ ማለላቸው አገር አንተ በዚህ ወገን
ፊት ትገባለህና ታወርሳቸውም አለህና ፡ በእስራኤል ፊት
ጨክን በርታ አለው ። ዘዳ፡ ፱ ፫ ።
እግዚአብሔርም ካንተ ጋራ በረድኤት ይኖራልና አይ
ለይህም አይንቅህምና አትፍራ አትደንግጥ አለው ።
ሙሴም ይህን የሕግን ነገር በመጽሐፍ ጽፎ የሕጉ
ማደሪያ ታቦትን ለሚሸከሙ ለሌዊ ልጆች ለካህናት ለእስ
ራኤል ልጆች አለቆችም ሰጣቸው ። ዘዳ፡ ፲፯ ፲፰ ።

፲ ወአዘዞሙ ሙሴ በይእቲ ዕለት ወይቤ እምድኅረ ስድስቱ ዓመት በዓመተ ኅድገት አመ በዓለ መጸለት ።

፲፩ አመ የሐውር ኵሉ እስራኤል ከመ ያስተርኢ ቅድመ እግዚአብሔር አምላክከ ውስተ መካን ዘኀረየ እግዚአብሔር አንብብዎ ለዝንቱ ሕግ ቅድመ እግዚአብሔር ።

፲፪ አስተጋብእዎሙ ለሕዝብ ከመ ይስምዑ እደዊሆሙ ወአንስቲያሆሙ ወደቂቆሙ ፡ ወግዩራን እለ ውስተ ሀገርክሙ ከመ ይስምዑ ወያእምሩ ፈሪሆቶ ለእግዚአብሔር አምላክሙ ወሰሚዖሙ ከመ ይግበሩ ኵሎ ሕጎ ለዝንቱ ቃል ።

፲፫ ወደቂቆሙኒ እለ ኢየአምሩ ይስምዑ ወይትመሀሩ ፈሪሆቶ ለእግዚአብሔር አምላክሙ በኵሉ መዋዕሊሆሙ ዘየሐይዉ እሙንቱ ዲበ ምድር እንተ ውስቴታ ተሀድዉ ዮርዳኖስ እንተሙ ከመ ትትዋረስዋ በህየ ።

፲፬ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለሙሴ ናሁ ቀርበ መዋዕለ ሞትከ ጸውዖ ለኢያሱ ወቁሙ ኀበ ኆኅተ ደብተራ ዘመርጡል ወአዝዞ ፡ ወሖሩ ሙሴ ወኢያሱ ውስተ ደብተራ ዘመርጡል ፡ ወቆሙ ኀበ ኆኅተ ደብተራ ዘመርጡል ።

፲፭ ወወረደ እግዚአብሔር በዐምደ ደመና ወቆመ ኀበ ኆኅተ ደብተራ ዘመርጡል ፡ ወቆመ ዐምደ ደመናሂ ኀበ ኆኅተ ደብተራ ዘመርጡል ።

፲፮ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለሙሴ ናሁ ትነውም አንተ ምስለ አበዊከ ወይትነሣእ ዝንቱ ሕዝብ ወይዜምዉ ድኅረ አማልክተ በዐድ ዘውስተ ምድር እንተ ውስቴታ ይበውኡ ወየኀድጉኒ ወይትዔወሩ ኪዳንየ ዘተካየድክዎሙ ።

፲፯ ወእትመዓዕ መዐተ በላዕሌሆሙ በይእቲ ዕለት ወእኀድጎሙ ወእሜይጥ ገጽየ እምኔሆሙ ወይከውኑ መብልዐ ለፀሮሙ ወትረክቦሙ ብዙኃት እኪት ወሥቃይ ፡ ወይብሉ በይእቲ ዕለት ፡ እስመ ኀደገነ እግዚአብሔር አምላክነ ወኢሀለወ ምስሌነ ረከበተነ ዛቲ እኪት ።

፲፰ ወአንሰ መይጠ እሜይጥ ገጽየ እምኔሆሙ በይእቲ ዕለት በእንተ ኵሉ ኃጣውኢሆሙ ዘገብሩ ወገብኡ ኀበ አማልክተ በዐድ ።

፲፱ ወይእዜኒ ጸሐፍ ኀገረ ለዛቲ ማኅሌት ወመሀርዎሙ ኪያሃ ለደቂቀ እስራኤል ወይደይዋ ውስተ አፉሆሙ ከመ ትኩነኒ ዛቲ ማኅሌት ስምዐ ላዕለ ደቂቀ እስራኤል ።

፳ እስመ አበውኦሙ ውስተ ምድር ቡርክት ዘመሐልኩ ለአበዊሆሙ ምድር እንተ ትውኅዝ ሐሊበ ወመዓረ ፡ ወበሊዖሙ ወጸጊቦሙ የዐብዱ ወይገብኡ ኀበ አማልክተ በዐድ ወያመልክዎሙ ወያምዕዑኒ ወየኀድጉ ኪዳንየ ።

፳፩ ወትቀውም ላዕሌሆሙ ዛቲ ማኅሌት ስምዐ ቅድመ ገጾሙ እስመ ኢትትረሳዕ እምውስተ አፉሆሙ ወእምውስተ አፈ ውሉዶሙ እስመ አነ አአምር እከዮሙ ኵሎ ዘይገብሩ በዝየ እንበለ አብኦሙ ውስተ ይእቲ ምድር ቡርክት ዘመሐልኩ ለአበዊሆሙ ።

፳፪ ወጸሐፈ ሙሴ ለዛቲ ማኅሌት በይእቲ ዕለት ወመሀሮሙ ኪያሃ ለደቂቀ እስራኤል ።

ሙሴም በዚያች ቀን ከስድስት ዓመት በኋላ ዳስ ሥራ በዓል በሚደረግበት ጊዜ በዓመተ ኅድገት ዘመን እንዲህ ብሎ አዘዛቸው ። ዘሌ፡ ፳፫ ፴፬ ፡ ዘዳ፡ ፲፭ ፩ ።

እግዚአብሔር በመረጠው ቦታ በፈጣሪህ በእግዚአብሔር ፊት ሊታይ እስራኤል ሁሉ በሄደ ጊዜ ፡ ይህን ሕግ በእግዚአብሔር ፊት አንብቡት ።

ሴቶችና ወንዶች በአገራችሁም ያሉ በደተኞች ልጆቻቸውም ሁሉ ይሰሙ ዘንድ የፈጣሪያቸው የእግዚአብሔርን አምልኮቱን ያውቁ ዘንድ ሰምተውም የዚህን ቃል ሥርዓት ሁሉ ይሠሩ ዘንድ ሕዝቡን ሰብስባችሁ አንብቡት አላቸው ። ዘዳ፡ ፬ ፲ ።

የማያውቁ ልጆቻቸውም በዚያ ትወርሷት ዘንድ ዮርዳኖስን በምትሻገሩባት ምድር እነሱቸው በሚኖሩበት ዘመን ሁሉ የፈጣሪያቸው የእግዚአብሔርን አምልኮቱን ሰምተው ይማሩ ዘንድ አንብቡት ብሎ አዘዛቸው ።

እግዚአብሔርም ሙሴን እነሆ የምትሞትበት ወራት ቀረበ ፡ ኢያሱን ጠርተህው ልዩ በሆነች ድንኳን ደጃፍ ቁሙ ችሁ እዘዘው ፡ ሙሴና ኢያሱም ልዩ ወደ ሆነች ድንኳን ሄደው በደብተራ ኦሪት ደጃፍ ቆሙ ።

እግዚአብሔር በዓምደ ደመና ወርዶ በደብተራ ኦሪት ደጃፍ ተገለጠ ፡ ዓምደ ደመናውም በደብተራ ኦሪት ደጃፍ ተተከለ ። ዘፀ፡ ፴፫ ፱ ።

እግዚአብሔርም ሙሴን እነሆ አንተ እንደ አባቶችህ ትሞታለህ ፡ ይህም ወገን ተነሥቶ እነሱ ገብተው በሚኖሩ በት አገር ያሉ የአሕዛብን ጣኦታት ያመልካሉ ፡ የተማማ ልኳቸው መሐላንም ቸል ይላሉ አለው ።

በዚያችም ቀን ቁጣን ተቈጥቼ እለያቸዋለሁ ገጽ - ረድኤቴንም ከነሱ እመልሳለሁ ፡ ለጠላቶቻቸውም ምግብ ይሆናሉ ፈጽሞ ብዙ መከራ ታገኛቸዋለች ፡ በዚያችም ቀን ፈጣሪያችን እግዚአብሔር ተለይቶናልና በረድኤትም ከኛ ጋር የለምና ይህች መከራ አገኘችን ይላሉ ።

እኔም ስለ ሠሩት ኃጢአታቸው ሁሉ የአሕዛብ ጣኦታትንም ስላመለኩ በዚያች ቀን ገጽ - ረድኤቴን ከነሱ ቸው እመልሳለሁ ። ዘዳ፡ ፴፩ ፲፯ ።

አሁንም የዚያችን ምስጋና ነገር ጽፈህ እሷን ለእስራኤል ልጆች አስተምሯቸው ፡ ይህችም ምስጋና (መዝሙር) በእስራኤል ልጆች ላይ ምስክር ትሆነኝ ዘንድ በቃላቸው ያስተምሯት ።

ተድላ ደስታ ወደምታስገኝ ለአባቶቻቸው ወደ ማልኩ ላቸው ምድር አገባቸዋለሁና በልተው ከጠገቡም በኋላ ይስታሉና ወደ አሕዛብ አማልክትም ተመልሰው ያመል ኳቸዋልና ቃል ኪዳኔንም አፍርሰው ያሳዝኑኛልና ።

ከነሳቸው እንደበትና ከልጆቻቸው አንደበት የምትዘ ነጋ ስለ ሆነ ፡ ለአባቶቻቸው ወደ ማልኩላቸው ወደዚያች ወደ ከበረች አገር ሳላገባቸው እኔ በዚህ የሚሠሩት ኃጢ አታቸውን ሁሉ አውቃለሁና ይህች ምስጋና (መዝሙር) በፊታቸው ምስክር ሁና ትነግባቸዋለች አለው ።

ሙሴም ያችን ምስጋና በዚያች ቀን ጽፎ ለእስራኤል ልጆች እሷን አስተማራቸው ።

፳፫ ወአዘዘ ሙሴ ለኢያሱ ወይቤሎ ጽናዕ ወትባዕ እስመ አንተ ታበውኦሙ ለደቂቀ እስራኤል ውስተ ምድር ዘመሐለ እግዚአብሐር ለአበዊሆሙ ወውእቱ ይሄሉ ምስሌከ ።

ሙሴም ኢያሱን የእስራኤል ልጆች እግዚአብሔር ላባቶቻቸው ወደ ማለላቸው ታገባቸዋለህና እሱም በረድኤት ከንተ ጋራ ይኖራልና ጨክን በርታ፥ ብሎ አዘዘው ።

፳፬ ወሶበ አኅለቀ ሙሴ ጽሒፎታ ለዛቲ ነገረ ሕግ ውስተ መጽሐፍ እስከ ፈጸማ አዘዞሙ ለሌዋውያን እለ ይፀውሩ ታቦተ ሕጉ ለእግዚአብሔር ።

ሙሴ እስኪ ጨርሳት ድረስ ደርሶ ይህችን የሕግን ነገር በመጽሐፍ ጽፎ በጨረሰ ጊዜ የእግዚአብሔር የሕጉ ማደሪያ ታቦትን የሚሸከሙ ሌዋውያንን ፤

፳፭ ወይቤሎሙ ንሥኡ ዘተ መጽሐፈ ወአንብርዋ ውስተ ክርሣ ለታቦተ ሕጉ ለእግዚአብሔር አምላክክሙ ወይንበር ህየ ስምዐ ለከ ።

ይህችን መጽሐፍ ወስዳችሁ በፈጣሪያችሁ በእግዚአብሔር በሕጉ ማደሪያ ታቦት ውስጥ አኑሯት፥ ላንተ ምስክር ይሆንህ ዘንድ በዚያ ይኑር ብሎ አዘዛቸው ።

፳፮ እስመ አነ አአምር ውሂከተከ ወክሳደከ ጽኑዐ ወእንዘ አነ ሀሎኩ ዓዲየ ሕያው ዮም አምዓዕክምዎ ለእግዚአብሔር፣ አፎኬ ፈድፋደ እም ድኅረ ሞትኩ ።

ቅሠፈኝ፥ ቅሠፈኝ ብለህ ማነማማትህን ክሳደ ልቡናህም ጽኑ እንደሆነ አውቃለሁና እኔ ገና በሕይወት ሳለሁ እግዚአብሔርን ያሳዘናችሁት ከሞትኩስ በኋላ እንዴት ፈጽማችሁ ታሳዝኑት ይሆን ! ። ዘፀ፥ ፴፪ ፱ ።

፳፯ አስተጋብኡ ኀቤየ ዐበይተ ነገድክሙ ወሊቃናቲክሙ ወመኳንንቲክሙ ወጸሐፍቲክሙ ከመ እንግሮሙ ይስምዑ ዘንተ ኵሎ ነገረ ወአስምዕ ላዕሌሆሙ ሰማየ ወምድረ ።

ይህን ሁሉ ነገር ይሰሙ ዘንድ እንድነግራቸው አለቆቻችሁና በወገኖቻችሁ ላይ የተሾሙ መኳንንቶቻችሁን ጸሐፊዎቻችሁን ዳኞቻችሁን ወደኔ ሰብስቡ፥ ሰማይንና ምድርን አስማባቸዋለሁ ። ዘዳ፥ ፲፯ ፲፰፥ ፴ ፲፱ ።

፳፰ እስመ አነ አአምር ከመ እምድኅረ ሞትኩ አብሶ ትኤብሱ ወተኀድግዋ ለፍኖት እንተ አዘዝኩክሙ ወትመጽእ ላዕሌክሙ እኪት በደኃሪ መዋዕል እስመ ትገብሩ እኪተ ቅድመ እግዚአብሔር አምላክክሙ ከመ ታምዕዕዎ በግብረ እደዊክሙ ።

ከሞትኩ በኋላ ፈጽማችሁ እንድትበድሉ ያዘዝኋችሁንም ሕግ እንድታፈርሷት እኔ አውቃለሁና በእጃችሁም ሥራ ታሳዝኑት ዘንድ በፈጣሪያችሁ በእግዚአብሔር ፊት ኃጢአት ትሠራላችሁና ኋላ በፍጻሜ ዘመን መከራ ትመጣባችኋለች ። ዘፍ፥ ፵፱ ፩፥ ዘዳ፥ ፴፪ ፳፥ ፪ ፴ ።

፴ ወነገሮሙ ሙሴ ወአስምዖሙ ለኵሉ ማኅበረ እስራኤል ነገራ ለዛቲ ማኅሌት ፍጹመ ።

ሙሴም ለእስራኤል ወገኖች ሁሉ እውነት የሆነ የዚህች የምስጋና ነገር አሰምቶ ነገራቸው ።

ምዕራፍ ፴፪ ።

፩ ወይቤ አጽምእ ሰማይ ወእንግርከ፣ ወትስማዕ ምድር ቃለ አፉየ ።

ሰማይ ስማኝ ልንገርህ፥ ምድርም ከአፌ የወጣውን ቃል ትስማ ።

፪ ወተወከፍዎ ከመ ነጠብጣብ ለነገርየ ወይረድ ከመ ጠል ነቢብየ፣ ወከመ ዝናም ውስተ ገዳም፣ ወከመ ጊሜ ውስተ ማዕር ።

ምድር ዝናምን እንድትቀበለው እናንተም ነገሬን ተቀበልዋት፥ ጠል ከሰማይ ወርዶ ከምድር እንዲስማማ ነገሬም ከልቡናችሁ ገብቶ ይስማማ፥ ዝናም በምድረ በዳ ወርዶ እንዲስማማ፥ ካፊያም ከመስክ ወርዶ እንዲስማማ ነገሬም ከልቡናችሁ ይስማማ አለ ። ኢሳ፥ ፶፭ ፲ ።

፫ እስመ ስመ እግዚአብሔር ጸዋዕኩ፣ ሀቡ ዕበየ ለአምላክነ ።

የእግዚአብሔርን ስም ጠርቻለሁና ለፈጣሪያችን ምስጋና አቅርቡ ። መዝ፥ ፸፱ ፮ ።

፬ እግዚአብሔር ጻድቅ በምግባሩ፣ ወርቱዕ ኵሉ ፍናዊሁ፣ እግዚአብሔር ጻድቅ ወአልቦ ዐመፃ፣ ጻድቅ ወኄር እግዚአብሔር ።

እግዚአብሔር በሥራው ሁሉ እውነተኛ ነው፥ ሥራውም ሁሉ የቀና ነው፥ እግዚአብሔር እውነተኛ ነው፥ ሐሰትም የለበትም እግዚአብሔር እውነተኛና ቸርም ነው ።

፭ አበሱ ወአኮ ሎቱ ትውልድ ርኩሳን ትውልድ ዕሉት ወግፍትዕት ከመዝኑ ተዐሥይዎ ለእግዚአብሔር ።

አደፈኞች ልጆች በደሉ፥ ነገር ግን እሱን የጐዱ አይደለም፥ ወንጀለኞች ገልበጥባጣም ልጆች ናቸው፥ ለእግዚአብሔር እንዲህ ያለ ወረታ ትመልሱለታላችሁን ፤ ።

፮ ዝ ሕዝብ ዐብድ ወአኮ ጠቢብ፣ አኮኑ ውእቱ አቡከ ዘፈጠረከ፣ ፈጠረከሂ ወገብረከ ።

ይህ ወገን ሰነፍ ነው፥ ዕውቀትም የሌለው አላዋቂ ነው፥ የፈጠረህ አምላክህ እግዚአብሔር አይደለምን ፤ ።

፯ ተዘከሩ መዋዕለ ትካት፣ ወለብዉ ዓመተ ትውልደ ትውልድ፣ ተሰአሎ ለአቡከ ወይነግረከ ወለአእሩጊከ ወይዜንዉከ ።

የድሮውን (የኖኅን) ዘመን አስቡ፥ ለልጅ ልጅ ጸንቶ የሚኖር ዘመንንም አስተውሉ፥ አባትክን ጠይቀው ይነግርሃል፥ ሽማግሎችንም ጠይቃቸው ይነግሩሃል ።

፰ አመ ከፈሎሙ ልዑል ለአሕዛብ ወዘከመ ዘርአሙ ለደቂቀ አዳም፣ ወአቀመ አድባሪሆሙ ለአሕዛብ ወበበኍልቈ

እግዚአብሔር አሕዛብን በቦታ እንደ ለያቸው የአዳምንም ልጆች እንደ በተናቸው እግዚአብሔርን በሚያገለ

| | | |
|---|---|---|
| ቆሙ ለመላእክተ እግዚአብሔር ። | | ግሉ በመላእክት ቍጥር የሕዝብን አውራጃዎች እንደ ወሰናቸው ይነግሩኻል ። |
| ወኮነ ያዕቆብ መክፈልተ ሕዝቡ ለእግዚአብሔር ፡ ወእስራኤልኒ ሐብለ ርስቱ ። | ፱ | ያዕቆብም ለእግዚአብሔር ዕድልነት ያለው ወገን ሆነ እስራኤልም ርስትነት ያለው ወገን ሆነ ። |
| ወአቀበሙ በውስተ በድው በውስተ ፋልል ፡ በሐሩር ወበጽምእ ፡ ሐፀሮሙ መገቦሙ ወመርሖሙ ወአቀቦሙ ከመ ብንተ ዐይን ። | ፲ | (ፋልል) ወዝ በሌለበት ምድረ በዳ ጠበቃቸው ውኃ ጥምና ድርቅ በጠናበት ጠበቃቸው መና ከደመና አውርዶ እየመገበ በደመና መራቸው እንደ ዓይን ብሌንም ጠበቃቸው ። |
| ወከመ ንስር ዘይከድን ወያስተጋብእ እጕሊሁ ታሕተ ክነፊሁ ፡ ወከመ የሐቅፍ እጕሊሁ በገበዋቲሁ ፡ ወሐዘሎሙ በክነፊሁ ወፆሮሙ በአንግድዓሁ ። | ፲፩ | አሞራ ገላግልቱን በክንፉ እንደሚሠውር በክንፈ ረድኤቱ ሠወራቸው ፡ በጕኑም ገላግልቱን እንዲያቅፍ በገበ ረድኤቱ አቅፎ አወጣቸው ። ዘፀ ፲፱ ፬ ። |
| እግዚአብሔር ባሕቲቱ መርሖሙ ወአልቦ ምስሌሆሙ አምላክ ነኪር ። | ፲፪ | እግዚአብሔር ብቻውን መራቸው ከነሱቸው ጋር ሌላ አምላክ አልነበረም ። |
| ወአዕረጎሙ ዲበ ኀይለ ምድር ወሴሰዮሙ እክለ ገራውህ ወሐፀኖሙ በመዓር እምኰኵሕ በቅብዕ እምእብን ጽንዕት ። | ፲፫ | ከምድር ወደሚገኘው አዝመራ አውጥቶ የእርሻዎች እኽልን መገባቸው ፡ ከማን በተገኘ ማር ከጭንጫማው ድንጋይም በተገኘ ቅቤ መገባቸው ። ኢሳ ፶፰ ፲፬ ። |
| በቅብዐ ላሕም ወበሐሊበ በግዕ ምስለ መቍዓለ ጠሊ ወላሕም እጐለ አልሕምት ወአበግዕ ምስለ ቄቅሐ ሥርናይ ወደመ አስካል ሰትዩ ወይነ ። | ፲፬ | ከላሙና ከፍየሉ ወረሞ ጋር በበግ ወተትና በላሙ ቅቤ አሳደጋቸው ልጠ ጕርዶ ከወጣለት ሥንዴ ጋራ የበጎችንና የላሞችን ጊደር ወተት መገባቸው ፡ የዘለላውንም ደም ወይን አድርገው ጠጡ ። መዝ፡ ፹፩ ፲፮ ። |
| በልዐ ያዕቆብ ወጸግበ ፡ ከረሮ ጽጋብ ለምንዙን ፡ ሰብሐ ወገዝፈ ወርኅበ ፡ ወኀደጎ ለእግዚአብሔር ፈጣሪሁ ወርኀቀ እምእግዚአብሔር ሕይወቱ ። | ፲፭ | ያዕቆብም በልቶ ጠግቦ የተወደደ (ያዕቆብን) ጥጋብ አቀናጣው ፡ ወፈረ ደነደነ ሰባ ፡ ፈጣሪው እግዚአብሔርን ተወው ፡ እነዋወሩም ከእግዚአብሔር ራቀ ። |
| ወወሀኩኒ በዝ ነኪር ፡ ወአምረሩኒ በርኵሶሙ ። | ፲፮ | በዚህ በጣኦቱ ቅሠፈኝ ቅሠፈኝ ብለው አነግሡኝ በር ኵሰታቸውም አስቈጡኝ (አሳዘኑኝ) ። |
| ሦዑ ለአጋንንት ወአኮ ለእግዚአብሔር ፡ ለአማልክት እለ ኢየአምርዎሙ አማልክተ ግብት እለ ይትገበሩ ወኢይበቍዑ ወእለ ኢየአምሩ አበዊሆሙ ። | ፲፯ | ለእግዚአብሔር ያይደለ ለአጋንንት መሥዋዕት ሠዉ ለማያውቋቸው አማልክት ተሠርተው ለማይረቡ ለማይጠቅሙ አባቶቻቸው ለማያውቋቸው ድንገት ለተገኙ ጣኦታት ሠዉ ። መዝ፡ ፲፮ ፴፯ ። |
| ኀደጎ ለእግዚአብሔር ፡ ዘወለደከ ወረሳዕከ ለእግዚአብሔር ዘሐፀነከ ። | ፲፰ | የፈጠረህ እግዚአብሔርን ተውከው ተከበከበ ያሳደገህ እግዚአብሔርንም ዘነጋኸው ። ኢሳ፡ ፲፯ ፲ ። |
| ወርእየ እግዚአብሔር ወቀንአ ወተምዐ መዐተ ላዕለ ደቂቆሙ ወአዋልዲሆሙ ። | ፲፱ | እግዚአብሔርም ይህን አይቶ ለአምላክነቱ ቀና በሴት ልጆቻቸውና በወንዶች ልጆቻቸውም ተቈጣ ። |
| ወይቤ እመይጥ ገጽየ እምኔሆሙ ወአሬእዮሙ ዘይከውኑ በደኃሪቶሙ ፡ እስመ ውሉድ ዓላውያን እሙንቱ ውሉድ እለ አልቦሙ ሃይማኖት ። | ፳ | ገጸ ረድኤቱን ከነሱቸው እመልሳለሁ ፡ ሃይማኖት የሌላቸው ወንጀለኞች ልጆች ናቸውና ፡ ኋላ በፍጻሜ ዘመን ምን እንዲሆኑ አያቸዋለሁ አለ ። ዘዳ፡ ፴፩ ፲፯ ። |
| እሙንቱሰ አቅንኡኒ በዘኢኮነ አምላክ ፡ ወአምዕዑኒ በአማልክቲሆሙ ፡ ወአነ አቀንኦሙ በዘኢኮነ ሕዝብ ፡ ወአምዕዖሙ በሕዝብ ዘኢይሌብዉ ። | ፳፩ | እነሱቸውስ አምላክ ባይደለ ጣኦት አስቀኑኝ በአማልክቶቻቸውም አሳዘኑኝ እኔም ባልሆነ ወገን አስቀናቸዋለሁ ያጠፋናል ብለው ልብ በማያደርጓቸው ወገኖች አሳዝናቸዋለሁ ። መዝ፡ ፴ ፮፡ ሆሴ፡ ፩ ፱ ። |
| እስመ እሳት ትነድድ እመዐትየ ወታውዒ እስከሲኦል ታሕተ ወትበልዓ ለምድር ወለኵሉ ፍሬሃ ወታነድድ መሠረታተ አድባር ። | ፳፪ | ከቁጣዬ የተነሣ (እሳት) ድርቅ ትሆናለችና ሥር መሠረት ትነቅላለች ፡ ከፍሬዋም ሁሉ ጋር ምድርን ታጠፋለች የተራራዎችንም መሠረት ታደርቃለች ። |
| ወአስተጋብእሙ ለእኪት ፡ ወአኀልቅ አሕፃየ በላዕሌሆሙ ፡ ወየኀልቁ በረኀብ ፡ ወይከውኑ መብልዐ ለአዕዋፈ ሰማይ ። | ፳፫ | ለመከራ እሰበስባቸዋለሁ ፡ በጦርም አጠፋቸዋለሁ ፡ በረኃብ አልቀው በሰማይ ለሚበሩ ወፎች ምግብ ይሆናሉ ። |
| ወይደክም ጽንዖሙ ፡ ወእፌኑ ላዕሌሆሙ ስነነ አራዊተ ምድር ምስለ ሕምዝ ከመ ይጕየዩ እምድር ። | ፳፬ | ኀይላቸው ይደክማል ከዚህ ዓለም ይጠፉ ዘንድ ከመርዝ ጋራ የምድር አበቦች ጥርሶችን እሰድባቸዋለሁ ። |

፳፭ በአፍአ ያጸምቶሙ መጥባሕት ለውሉዶሙ ወበውስተ አብያቲሆሙ ድንጋፄ ለወራዙቶሙ ምስለ ደናግሊሆሙ ፤ ለሕፃናቲሆሙ ምስለ አእሩጊሆሙ ።

ልጆቻቸውን በዘመቻ ጦር ያጠፋቸዋል ፡ ጐልማሶቻቸውን ከቆነጃጅቶቻቸው ጋር ሽማግሌዎቻቸውን ከልጆቻቸው ጋራ በቤቶቻቸው ድንጋጤ ያጠፋቸዋል ።

፳፮ ወእቤ ከመ እዝርዎሙ ፡ ወእስዐር እምድር ዝክሮሙ ፡ ወእምእጓለ እመሕያው ።

አጠፋቸው ዘንድ ላጥፋቸው አልኩ ፡ ከሰው ለይቼ ከዚህ ዓለም ስም አጠራራቸውን አጠፋ ዘንድ ላጥፋቸው አልኩ ። ሕዝ፡ ፴ ፲፫ ።

፳፯ በመዐት ፀረ ከኑኒ ከመ ኢይትዐበዩ ፀር ፡ ወኢይበሉ እዴነ ጸንዐት አኮኑ እግዚአብሔር ዘገብሮ ለዝ ኵሉ ።

ጣኦትን በማምለክ ጠላቶች ሆኑኝ ፡ አሕዛብ እንዳይታበዩና ሥልጣናችንም በእስራኤል ላይ ጸና እንዳይሉ ይህን ሁሉ ያደረገ እግዚአብሔር አይደለምን፤ ለምን ይታበያሉ ። ዘኍ፡ ፲፱ ፲፮ ፡ ኤር፡ ፲፱ ፬ ።

፳፰ እስመ ሕዝብ ሕጉላነ ምክር እሙንቱ ፡ አልቦሙ ምልሕ ወኢሃይማኖት ።

ምክር ያጡ ወገኖች ናቸው ፡ ምግባርም ሃይማኖትም የሌላቸው ወገኖች ናቸውና ።

፳፱ ወኢሐለይዎ ከመ ያእምርዎ ለዝንቱ ወኢየአምርዎ በመዋዕል ዘይመጽእ ።

ይህንም ሊያውቁት አላሰቡትም በሚመጣውም ዘመን የሚሆነውን አላወቁም ነበር ።

፴ እፎ ያነትዎሙ እሐዱ ለዐሠርቱ ምእት ፡ ወክልኤቱ ይሰድድዎሙ ለእልፍ ፡ እስመ እግዚአብሔር ፈደዮሙ ወእምላክነሂ አግብኦሙ ።

ቢያውቁማ ኖሮ እግዚአብሔር ፍዳውን አምጥቶባቸዋልና ፈጣሪያችንም በአሕዛብ እጅ ጥሏቸዋልና ፡ አንዱ ሰው እንዴት ሺሑን ያሳድዳቸው ነበር! ሁለቱስ እንዴት ዓሥሩን ሺሕ ያሸሹዋቸው ነበር! ። ፩ ሳሙ፡ ፱ ፱፡ ፬ ፳ ።

፴፩ እስመ ኢኮነ አምላክነ ከመ አማልክቲሆሙ ፡ ፀርነሰ ዓብዳን ።

ፈጣሪያችን እንደ አማልክቶቻቸው አይደለም እኮ! ጠላቶቻችን ግን ሰነፎች ናቸው ።

፴፪ እስመ ከመ ዐፀደ ወይነ ሰዶም ዐፀደ ወይኖሙ ፡ ወሐረጎሙኒ እምነ ገሞራ ወአስካሎሙኒ አስካለ ሐሞት ፡ ወቀምሐሙኒ መሪር ።

የሕጋቸው ማደሪያ የሆነ ልባቸው እንደ ሰዶም ሕግ ማደሪያ ነውና ፡ ወገናቸውም ከገሞራ ወገን ነውና ፡ ሕጋቸውም የሚያጠፋ ሕግ ነውና ዘለላውም መራራ ነውና ፡ ሰነፎች ናቸው ።

፴፫ ሕምዘ አርዌ ምድር ወይኖሙ ሕምዘ አፍዖት ዘይቀትል ።

ሕጋቸው የምድር እባብ መርዝ ነው ፡ የሚገድልም የፍኝት መርዝ ነው ። ኢያ፡ ፳፬ ፲፰ ፡ መዝ፡ ፶፰ ፬ ።

፴፬ አኮኑ ዝንቱ ትእዛዝ ዘእምኀቤየ ውእቱ ወተኀትመ ውስተ መዛግብትየ ።

ይህ ትእዛዝ በኔ ዘንድ ተጠብቆ የለምን፤ አሕዛብስ በመዝገቤ የታተሙ አይደሉምን፤ ። ኢዮ፡ ፲፬ ፲፮ ።

፴፭ በዕለተ ኵነኔየ እትቤቀሎሙ ወበጊዜ ይድኀፅ እግሮሙ እስመ ቀርበ ዕለተ ኀርትምናሆሙ ፡ እስመ በጽሐት ወድልውት ይእቲ ለክሙ ።

የሚጐሰቁሉበት ቀን ቀርቧልና የሚጠፉበትም ቀን ደርሷልና እግራቸው የሚሰናከሉበትም ጊዜ ይህች ለነሱ የተዘጋጀች ናትና ፍርድ በሚደረግበት ቀን እበቀላቸዋለሁ።

፴፮ እስመ ይፈትሕ እግ ኢአብሔር ለሕዝቡ ፡ ወይትናበብ በእንተ አግብርቲሁ ፡ እስመ ርእዮሙ ከመ ተመስዉ ወኀልቁ ወተዘንጐጉ በኀበ ሀለዉ ።

እግዚአብሔር ለወገኖቹ ለእስራኤል ይፈርዳልና ፡ ስለ ባሮቹም በአሕዛብ ይናገርባቸዋልና እበቀላቸዋለሁ አለ ፡ እሊህ እስራኤል እንደ ሰም ቀልጠው እንደጠፉ በያሉበትም እንደተሸሟጠጡ አይቷቸዋልና ።

፴፯ ወሰበ ሠርሐ ይቤ እግዚአብሔር አይቴ እሙንቱ አማልክቲክሙ እለ ትትዌከሉ ቦሙ ።

በመከራው ተይዘው በደከሙም ጊዜ ፡ እግዚአብሔር የምታምኑባቸው አማልክቶቻችሁ ወዴት ናቸው! ።

፴፰ ወእለ ትበልዑ መሳብሕተ መሥዋዕቶሙ ፡ ወትሰትዩ ወይነ ሞጻሕቶሙ ፡ ይትንሥኡኬ ወይርድኡክሙ ወይኩኑክሙ መድኀኒክሙ ።

የመሥዋዕታቸውን ስብ የምትበሉላቸው ወይናቸውን ፍልቅ አድርጋችሁ የምትጠጡላቸው ጣኦቶቻችሁ ወዴት ናቸው፤ ተነሥተው ይርዷችሁ የሚያድኗችሁ ይሁኗ አለ ።

፴፱ አእምሩ አእምሩ ከመ አነ ውእቱ እግዚአብሔር ወአልቦ ባዕድ አምላክ ዘእንበሌየ ፡ አነ እቀትል ወአሐዩ ፡ እቀሥፍሂ ወእሣሀል ፡ ወአልቦ ዘያመስጥ እምእዴየ ።

እንዚህንስ ትታችሁ ፈጣሪያችሁ እኔ እንደሆንኩ ያለ እኔም ሌላ ፈጣሪ እንደሌለ ዕወቁ! ዕወቁ! እኔ እገድላለሁ ፡ አድንማለሁ በመከራው እገርፋለሁ ፡ ይቅርም እላለሁ ፡ ከእጄ የሚያመልጥም የለም ። መዝ፡ ፺፱ ፳፮ ።

፵ እስመ አሌዕል ውስተ ሰማይ እዴየ ፡ እምሕል በየማንየ ወእብል ሕያው አነ ለዓለም ።

እጄን ወደ ሰማይ ዘርግቼ ለዘለዓለም ሕያው ነኝ ብዬ በሥልጣኔ እምላለሁ ። ዘኍ፡ ፲፬ ፴ ።

፵፩ ወአበልሖ ከመ መብረቅ ለመጥባሕትየ ፡ ወትቀውም እዴየ በኵነኔየ ወእትፈደዮሙ በቀለ ለፀርየ ወእትቤቀሎሙ ለጸላእትየ ።

ሥልጣኔን እንደ መብረቅ አሳጥናታለሁ ፡ ሥልጣኔም በፍርዴ ትጸናለች ጠላቶቼን ተበቅዬ አጠፋቸዋለሁ ፡ ጠላቶቼን እበቀላቸዋለሁ ። መዝ፡ ፯ ፲፱ ፡ ሕዝ፡ ፳፩ ፱ ።

፵፪ ወእሰክሮን በደሞሙ ለአሕጻየ ወትበልዕ ሥጋሆሙ መጥባሕትየ እምደመ ቅቱላን ወፂዉዋን እርእሰተ መላእክተ ፀር ።

፵፫ ይትፌሥሑ ኵሉን ሰማያት ኅቡረ ወይሰግዱ ሎቱ ኵሉሙ መላእክተ እግዚአብሔር ወይትፌሥሑ አሕዛብ ምስለ ሕዝቢሆሙ ፣ ወይብሉ ኵሎሙ ውሉደ እግዚአብሔር ጽኑዕ ውእቱ ።

፵፬ እስመ ይትቤቀል ደመ ደቂቁ ይትቤቀል ወይትፈደዮሙ በቀለ ለፀሩ ፣ ወይትቤቀሎሙ ለጸላእቱ ፣ ወያነጽሕ እግዚአብሔር ምድረ ለሕዝቡ ።

፵፭ ወጸሐፈ ሙሴ ለዛቲ ማኅሌት በይእቲ ዕለት ወመሀሮሙ ለደቂቀ እስራኤል ፣ ወቦአ ሙሴ ወነገሮሙ ለሕዝብ ወአስምዖሙ ውእቱ ወኢያሱ ወልደ ነዌ ።

፵፮ ወሶበ አኅለቀ ሙሴ ነጊሮቶሙ ለኵሉ እስራኤል ይቤሎሙ ዕቀብዎ በልብክሙ ለዝንቱ ኵሉ ነገር ዘአስማዕኩክሙ ላዕሌክሙ ዮም ፣ ዘትኤዝዙ ደቂቅክሙ ዮም ከመ ይዕቀቡ ወይግበሩ ኵሉ ነገሮ ለዝንቱ ሕግ ።

፵፯ እስመ ኢኮነ ከንቶ ዝንቱ ነገር ለክሙ ፣ እስመ ውእቱ ሕይወትክሙ ወበበይነ ዝ ነገር ይነውኅ መዋዕሊክሙ ውስተ ምድር እንተ ላቲ ተዐድዉ ዮርዳኖስ ከመ ትትዋረስዋ በህየ ።

፵፰ ወነበበ እግዚአብሔር ለሙሴ በይእቲ ዕለት ወይቤሎ ዕርግ ውስተ ደብረ አባሪም ዘውስተ ደብረ ናበር ዘምድረ ሞዓብ ዘመንገለ ገጸ ኢያሪኮ ፣ ወረአያ ለምድረ ከነዓን ዘእሁቦሙ ለደቂቀ እስራኤል ይምልክዋ ።

፵፱ ወሙት በውስተ ደብር ዘውስቴቱ ተዓርግ ህየ ፣ ወተወሰክ ኀበ ሕዝብከ ከመ ሞተ አሮን እኁከ በውስተ ደብረ ሆር ወአተወ ኀበ ሕዝቡ ።

፶ እስመ ክሕድክሙ ቃልየ በቅድመ ደቂቀ እስራኤል በኀበ ማየ ቅስት ዘቃዴስ በገዳም ዘጺን ፣ እስመ ኢቀደስክሙኒ በቅድመ ደቂቀ እስራኤል ።

፶፩ ወረእያ ለይእቲ ምድር ቅድሜከ ወህየሰ ኢትበውእ ።

ምዕራፍ ፴፫ ።

፩ ወከመዝ ይእቲ በረከት ዘባረኮሙ ለደቂቀ እስራኤል ሙሴ ብእሴ እግዚአብሔር ዘእንበለ ይሙት ።

፪ ወይቤ እግዚአብሔር እምነ ሲና ወዕአ ወመጽአ ወአስተርአየነ በሴይር ፣ ወአፅረፈ በደብረ ፋራን ምስለ አእላፈ ቃዴስ እለ እምየማኑ መላእክቲሁ ወእለ ምስሌሁ ።

፫ ወምሕኮሙ ለሕዝቡ ወለኵሎሙ እለ ተቀደሱ በእደሁ ፣ ወእሉሂ እሊአከ እሙንቱ ።

፬ ወረከቡ ሕገ በቃለ ዚአሁ ዘአዘዘነ ፣ ወርስተ ለሕዝበ ያዕቆብ ።

፭ ወይከውን መልአከ እምፍቁር ፣ ተጋቢኦሙ መላእክተ አሕዛብ ምስለ ነገደ እስራኤል ።

፮ አንሥኦ ለሮቤል ኢይሙትኒ ወይኩን ብዙኀ ኍልቈሁ ።

ፍላጻዎቼን በደማቸው አሰክራቸዋለሁ ፣ ሥልጣኔም ሰውነታቸውን ታጠፋለች ፣ ከተወጉትና ከተማረኩትም ደም ፍላጻዎቼን አሰክራለሁ ፣ ሾተሌም የጠላቶች አለቆች ቾብቾቦን ትቈርጣለች ። ኤር፡ ፵፮ ፲ ፣ መሰ፡ ፩ ፪ ።

ሰማያት ሁሉ (ልዑላን) አንድነት ደስ ይላቸዋል ፣ የእግዚአብሔር መላእክት (አለቆች) ሁሉ ይሰግዱለታል ፣ ወገኖች ከወገኖቻቸው ጋራ ደስ ይላቸዋል የእግዚአብሔርም ልጆች (እስራኤል) ሁሉ ጽኑ ነው ይላሉ ።

በልጆቹ ደም ተበቀሉ በጠላቶቹ ፍዳን ያመጣባቸዋል ጥንተ ጠላቶቹንም ይበቀላቸዋልና ፣ እግዚአብሔር ከነዓንን ለወገኖቹ (ለእስራኤል) የምትገበ አድርጎ ያወርሳቸዋል ።

ሙሴ በዚያች ቀን ይህችን (ማኅሌት) ምስጋና ጽፎ ለእስራኤል ልጆች አስተማራቸው ፣ ሙሴም ገብቶ እሱ አሰምቶ ለሕዝቡ ነገራቸው የነዌ ልጅ ኢያሱም አሰማቸው ።

ሙሴም ለእስራኤል ልጆች ነግሮ ከጨረሰ በኋላ ፣ ሕጉን ጠብቀው የዚችን የሕግ ነገር ሁሉ ያደርጉ ዘንድ ፣ ለልጆቻችሁ የምታዝዙት እኔ አሁን ያሰማኋችሁና ይህን ሁሉ ነገር በልባችሁ (ጠብቁት) አስተውሉት ።

እሱ ሕይወታችሁ ስለሆነ ይህ ነገር ለናንተ ከንቱ አይደለምና ፣ ስለዚህ ነገር ትወርሷት ዘንድ ዮርዳኖስን በምትሻገሩላት አገር ዘመናችሁ በዚያ ይበዛል ። ምሳ፡ ፫ ፪ ። ሮሜ ፲ ፭ ።

እግዚአብሔርም በዚያች ቀን ሙሴን እንዲህ ሲል ተናገረው ፣ በኢያሪኮ አንጻር በሞዓብ አውራጃ በናቦር ተራራ ወዳለ ወደ አባሪም ተራራ ወጥተህ ይገዟት ዘንድ ለእስራኤል ልጆች የምሰጣቸው ከነዓንን እያት ።

ወንድምህ አሮን ሖር በሚባል ተራራ ሙቶ ወደ ወገኖቹ እንደተጨመረ አንተም ወደ ምትወጣበት ተራራ ወደ ወገኖችህ ተጨመር ። ዘኁ፡ ፳ ፳፰ ።

ጺን የሚባል ዕንጨት ባለበት በቃዴስ ምድረ በዳ ጠብ ክርክር በተደረገበት ውኃ ቃሌን ስለ ካዳችሁ በእስራኤል ልጆች ፊት አላመሰገናችሁኝምና ።

በፊትህ ያለች ያችንም ምድር እያት ፣ ወደዚያ ግን አትገባም ብሎ ለሙሴ ነገረው ። ዘዳ፡ ፫ ፳፪ ።

ምዕራፍ ፴፫ ።

የእግዚአብሔር ሰው ሙሴ ሳይሞት የእስራኤልን ልጆች የመረቃቸው ምርቃት እንዲህ ናት ። ዘፍ፡ ፵፱ ፳፰ ።

እግዚአብሔር ከደብረ ሲና ወጥቶ መጥቶ በሴይር ተገለጠልኝ ፣ ከሱም ጋር ያሉ መላእክት በቀኙ ያሉ እግዚአብሔር ከእስራኤል ጋር በፋራን ተራራ (በረድኤት) ዐረፈ አለ ።

በቃሉ ለተለዩ (ሌዋውያን) ሁሉና ለወገኖቹም (እስራኤል) ራራላቸው ፣ እነዚህም (ሌዋውያን) ወገኖችህ ናቸው ።

ባዘዘን ቃሉም ሕጉን አገኙ (ጠበቁ) ለያዕቆብም ወገኖች ሕጉ ርስት ሁኖ ተሰጣቸው ። ዮሐ፡ ፯ ፲፱ ።

ከወዳጅ (ከያዕቆብ) ዳዊት ይወለዳል ፣ የአሕዛብም አለቆች ከእስራኤል ወገኖች ጋራ አንድ ሁነው ይገዙለታል ።

በነፍስ እንዳይሞትብኝ ሮቤልን (በጸሎት) እፈልገዋለሁ ቍጥሩም ብዙ ይሁን ። ዘፍ፡ ፵፱ ፬ ።

፯ ወለዝንቱኒ ይሁዳ ስምዖ እግዚኦ ቃሎ ለይሁዳ ፡ ወይግባእ ውስተ ሕዝቡ ፡ ወእደዊሁ ይኩንናሁ ፡ ወኩኖ ረዳኤ እምፀሩ ።

ይህንን ይሁዳን ነገር አድርጎ ተናገረው አቤቱ ! የይሁዳ ጸሎቱን ስማ ፡ ወደ ወገኖቹም ይመለስ ፡ ሥልጣኖቹም ይግዙ ፡ ከጠላቶቹም ረዳት ሁነው ።

፰ ወለሌዊኒ ይቤሎ አግብእ ለሌዊ ቃሎ ወጽድቆ ለብእሲ ጻድቅ ዘአመከርዎ በመከራ ፡ ወጸአልዎ በኀበ ማየ ቅስት ።

ሌዊንም ነገር አድርጎ ተናገረው ፡ በመከራ ለፈተኑት ጠብ ክርክር በተደረገበትም ውኃ ለሰደቡት ።

፱ ዘይቤሎሙ ለአቡሁ ወለእሙ ኢርኢኩክሙ ወበአኀዊሁኒ ኢያእመረ ወበደቂቁኒ ኢለበወ ወዐቀበ ቃለከ ፡ ወተማኅፀነ ኪዳነከ ።

እናት አባቱን አላየኋችሁም ላላቸው በወንድሞቹ (በእስራኤል) የሚደረገውን (ፍቅር) ላላወቀ በልጆቹም የሚደረገውን ላላስተዋለ ቃልህን ለጠበቀ በቃል ኪዳንህም የተማጠነ ። ዘፀ፡ ፴፰ ፴ ፡ ፲፯ ፯ ፡ መዝ፡ ፻፯ ፲፯ ።

፲ ከመ ይንግሩ ሥነኒከ ለያዕቆብ ወሕገከ ለእስራኤል ወከመ ይደዩ ዕጣነ በማዕጠንትከ ወበኵሉ ጊዜ ውስተ ምሥዋዒከ ።

ሕምልከትህን ለያዕቆብ ሕግህንም ለእስራኤል ያስተምሩ ዘንድ በጥናህም ዕጣንን ይጨምሩ ዘንድ ፡ በመሠውያህም በየጊዜው መሥዋዕትን ይሠዉ ዘንድ ፡ እውነተኛ ለሆነ ሰው ለሌዊ የትሩፋቱን ዋጋ ስጠው ።

፲፩ ወባርክ እግዚኦ ኀይሎ ፡ ወተወከፍ ግብረ እደዊሁ ፡ ወእውርድ ክበደ ላዕለ እለ ይትቃወምዎ ፀሩ ፡ ወኢታንሥኦሙ ለእለ ይፃረርዎ ።

አቤቱ ! ሠራዊቱን አብዛ በቃሉ የጸለየውንም ጸሎት ተቀበል ፡ በሚከራከሩት ጠላቶቹም መከራ አምጣባቸው የሚጣሉት ጠላቶቹንም በረድኤት አታድናቸው ።

፲፪ ወለብንያምኒ ይቤሎ ፡ ፍቁረ እግዚአብሔር የኀድር ተአሚኖ ፡ ወእግዚአብሔር ይጼልሎ በኵሉ መዋዕሊሁ ፡ ወየዐርፍ ማእከለ መታክፊሁ ።

ብንያምንም ነገር አድርጎ ተናገረው ፡ የእግዚአብሔር ወዳጅ ብንያም ከመከራው ተዘልሎ ይኖራል ፡ እግዚአብሔርም በዘመኑ ሁሉ ከመከራው ይሠውረዋል ፡ በወንድሞቹም መካከል ይኖራል ።

፲፫ ወለዮሴፍኒ ይቤሎ እምበረከተ እግዚአብሔር ምድሩ ወእምዝናመ ሰማይ ወጠል ወእምነቅዐ ቀላይ ዘእምታሕቱ ።

ዮሴፍንም ነገር አድርጎ ተናገረው ፡ ምድሩ ከእግዚአብሔር በተገኘ በረከት ጠልንና የሰማይ ዝናምን አግኝታ ከምድር የወጣ የመስኖ ውኃን ጠጥታ እኽልን ታበቅላለች ።

፲፬ ወለለሰዐቱ እክሉ ፡ ወእምሥርቀተ ፀሐይ ወእምነ ኀላቈሆሙ ለአውራኅ ።

ፀሐይ እየወጣ ፡ ወራት በባቱ ቍጥር እኽሉ በየሰዓቱ ነው ። ዘፍ፡ ፵፱ ፳፩ ።

፲፭ ወይቀድም እምአርእስተ አድባር ፡ ወእምውስተ አርእስተ አውግር ዘአኤናዎን ።

(አኤናዎን) ዘለዓለም ጸንተው ከሚኖሩ ከረብታዎችና ከተራሮች ራስ ቀርቦ ይታያል ። ዕንባ፡ ፫ ፮ ።

፲፮ ምድር እንተ ዘልፈ ጽግብት ወሠናይት ለዘአስተርአየ በውስተ ዕፀ ጳጦስ ለይምጻእ ዲበ ርእሱ ለዮሴፍ ወበርእሱ ይክበር በውስተ አኀዊሁ ከመ በኵረ ላሕም ስኑ ።

ምድሩ ሁል ጊዜ ዝናሙን ጠሉን የጠገበች ያማረች (የተወደደች) ናት ፡ ጳጦስ በሚባል ዕንጨት የታየ የእግዚአብሔር ረድኤት በዮሴፍ (ይምጣ) ይደር ፡ በወንድሞቹም መካከል በሥልጣኑ ይክበር ፡ መወደዱም ከላም መጀመሪያ እንደተወለደ ወይፈን ነው ። ዮሐ፡ ፮ ፴ ።

፲፯ ወእምአቅርንት ዘአሐዱ ቀርኑ አቅርንቲሁ ፡ ወይወግኦሙ ለአሕዛብ በሙ ኅቡረ እስከ አጽናፈ ምድር ዝንቱ አእላፍ ዘኤፍሬም ፡ ወዝንቱ አእላፍ ዘምናሴ ።

ቀንዱ አንድ እንደሆነ ርኤም በቀንዱ እንዲከብር በሥልጣኑ ይከብራል ፡ በምድር ዳርቻ ያሉ አሕዛብን በሥልጣኑ አንድነት ያጠፋዋቸዋል ፡ ይህ የኤፍሬም ወገን ነው ይባላል ፡ ይህም የምናሴ ወገን ነው ይባላል ።

፲፰ ወለዛብሎንኒ ይቤሎ ፡ ተፈሣሕ ዛብሎን በፀአትከ ፡ ወይሳኮር በማኅደርከ ፡ እለ ያጠፍእዎሙ ለአሕዛብ ።

ዛብሎንንም ነገር አድርጎ ተናገረው ፡ ዛብሎን ወደ ዘመቻ በመውጣትህ ደስ ይበልህ ይሳኮርም ከዘመቻ በመግባትህ ደስ ይበልህ እነዚህ አሕዛብን የሚያጠፉዋቸው ናቸው ።

፲፱ ወጸውዑ በህየ ወሦዑ መሥዋዕተ ጽድቅ እስመ ብዕለ ባሕር የሐፅነከ ወየሐንፀከ ፡ ወንዋዮሙ ለእለ ይነብሩ ውስተ ጰራልያ ።

እውነተኛ መሥዋዕትን ሠውተው በዚያ (በደብረ ታቦር) አመሰገኑ (የባሕር ሃብት) የአሕዛብን ገንዘብ ትመግብ ለህና ቤትህንም ያንጽልሃልና በደሴት የሚኖሩ የአሕዛብ ገንዘብ ያንተ ገንዘብ ነው ። ኢሳ፡ ፪ ፫ ፡ መዝ፡ ፬ ፭ ።

፳ ወለጋድኒ ይቤሎ ፡ ርኂብ በረከቱ ለጋድ ከመ አንበሳ የኀድር ቀጥቂጦ መዝራዕተ መላእክት ።

ጋድንም ነገር አድርጎ ተናገረው ፡ የጋድ ገንዘቡ ብዙ ነው የጠላቶቹን ክንድ አድቅቆ እንደ አንበሳ ተዘልሎ ይኖራል ። ዘፍ፡ ፵፱ ፬ ፡ ዘዳ፡ ፳፫ ፳፪ ።

፳፩ ወርእየ ቀድሚሁ ከመ በህየ ተከፈልዋ ለምድር መላእክት እንዘ ጉቡአን መሳፍንት ኅቡረ ምስለ መልአከ አሕ

ከእስራኤል ወገኖችና ከእስራኤል አለቃ (ከኢያሱ ጋር) ሹማምንት አንድነት ተሰብስበው አለቆች በዚያ እን

ዘብ ፡ ወምስለ ሕዝበ እስራኤል እግዚአብሔር ገብረ ጽድቆ ወኵነኔሁ ምስለ እስራኤል ።

ደተከፈሏት በፊቱ አየ ፤ እግዚአብሔር ፍርዱንና ቸርነቱን ከእስራኤል ጋር አደረገ ። ዘኁ ፴፪ ፩ ፥ ፳፩ ፲፰ ።

፳፪ ወለዳንሂ ይቤሎ ፡ ዳን እጓለ አንበሳ ፥ ወይሠርር እምነ በሳን ።

ዳንንም ነገር አድርጎ ተናገረው ፡ ዳን የአንበሳ ግልገል (ደቦል) ነው ፤ ከባሳን ዘሎ ይወጣል ፤ (ይዘምታል) ።

፳፫ ወለንፍታሌምኒ ይቤሎ ፥ ንፍታሌም ጽጉብ እምሠናያት ወይጸግብ እምበረከተ እግዚአብሔር ፥ ወይትዋረስ ባሕረ ወሊበ ።

ንፍታሌንም ነገር አድርጎ ተናገረው ፤ ንፍታሌም ከበጎዎች (ተድላ ደስታ) የጠገበ ነው ፤ የእግዚአብሔርን በረከት ይጠግባል (ያገኛል) ባሕሩንና ደቡቡን (፬ቱን መዓዝን) ይገዛል ። ዘፍ ፵፱ ፳፩ ፥ ሕዝ ፳ ፵፮ ።

፳፬ ወለአሴርሂ ይቤሎ ፡ ቡሩክ ውእቱ እምውሉደ አሴር ፥ ወይከውን ኅሩየ ለአኀዊሁ ወየሐጽብ በቅብዕ እገሪሁ ።

አሴርን ነገር አድርጎ ተናገረው ፡ አሴር ከእስራኤል ይልቅ የተመረቀ ነው ፡ ለወንድሞቹም የተመረጠ ይሆናል እግሮቹን በዘይት ይታጠባል ። ዘፍ ፵፱ ፳ ።

፳፭ ዘሐፂን ወዘብርት አሣእኒሁ ፥ ወይከውን በከመ መዋዕሊከ ኀይልከ ።

ጫማዎቹ የናስና የብረት ናቸው ፤ ኃይልህም እንደ ዘመንህ ነው ።

፳፮ አልበ ከመ አምላኩ ለፍቁር ዘይነብር ውስተ ሰማይ ውእቱ ረዳኢከ ወዕበየ ሥኑ ለሰማይ ።

በሰማይ እንደ ሚኖር እንደ እስራኤል ፈጣሪ ያለ የለም ፤ ረዳትህም እሱ ነው ፤ ዝናም ለዘር ጠል ለመከር የሚሰጥም እሱ ነው ። ዘፀ ፲፰ ፲፩ ፥ ዘዳ ፴፪ ፲፰ ።

፳፯ ወይከድንከ እግዚአብሔር ፍጽመ በኀይለ መዝራዕት አሌናዎን ወይወፅአ እምቅድመ ገጽከ ፀርከ ፥ በከመ ይቤ ከመ ያጥፍአሙ ።

እግዚአብሔር ፊታውራሪ ሁኖ በዘለዓለማዊ ክንዱ ኃይል ከመከራው ይሠውርሃል ፡ እግዚአብሔር ያጠፋቸው ዘንድ አጠፋቸዋለሁ ብሎ እንደ ተናገረ ጠላትህ ከፊትህ ይወጣል (ይጠፋል) ።

፳፰ ወያነብሮ ለእስራኤል ተአሚኖ ባሕቲቶ ውስተ ምድረ ያዕቆብ ፡ ውስተ ምድረ ሥርናይ ፥ ወወይን ፥ ወሰማይኒ ለከ ምስለ ደመና ወጠል ።

እስራኤልንም ወይንና ሥንዴ ባለበት በያዕቆብ አገር ብቻውን ተዘልሎ እንዲኖር ያደርገዋል ፤ ሰማይም ከጠልና ከደመና ጋር ላንተ ዝናም ይሰጣል ።

፳፱ ወብፁዕ አንተ እስራኤል መኑ ከማከ ሕዝብ ዘእግዚአብሔር ያድኅኖ ወያፀንዐከ ወይረድአከ ወበመጥባሕትከ እልገትከ ሕበው ፀርከ ወአንተ ትኪዐን ላዕለ ክሳዳቲሆሙ ።

እስራኤል ሆይ ፤ አንተ ንኡድ ክቡር ነህ እግዚአብሔር የሚያድነው እንዳንተ ያለ ማን ነው ፤ ይረዳሃል ያጸናሃል ፡ በሾተልህ ገድለህ ሰልበህ ኑር ፡ ጠላትህ አንተን አጠፋለሁ ማለቱ ሐሰት ነው ፤ አንተ ግን የጠላቶችህ አንገታቸውን ረግጠህ ትገዛቸዋለህ ። ፪ ሳሙ ፯ ፳፫ ።

## ምዕራፍ ፴፬ ።

፩ ወዐርገ ሙሴ እምአባሬም ዘሞዓብ ውስተ ደብረ ናበር ውስተ ርእሰ ፋስጋ ዘሀለወ ቅድመ ኢያሪኮ ፥ ወአርአዮ እግዚአብሔር ኵሎ ምድረ ገለአድ ፥ ወኵሎ ምድረ ንፍታሌም ወኵሎ ምድረ ምናሴ ፥ ወኵሎ ምድረ ይሁዳ እስከ ደኃሪት ባሕር ።

ሙሴ የሞዓብ ክፍል ከምትሆን ከአባሪም በኢያሪኮ አንጻር ወዳለ ወደ ፋስጋ ራስ ናበር ወደ ሚባለው ተራራ ወጣ ፤ እግዚአብሔርም የገለዓድንና የንፍታሌምን ምድር ሁሉ የምናሴንና የይሁዳን ምድር ሁሉ እስከ ባሕር መጨረሻ ድረስ አሳየው ። ዘዳ ፲፩ ፳፬ ።

፪ ወገዳሙ ወአድያሚሃ ለኢያሪኮ ሀገረ ፊንቆን እስከ ሴይር ።

የፊንቆን አገር የምትሆን የኢያሪኮንም አውራጃ እስከ ሴይር ድረስ አሳየው ። ፪ ሳሙ ፲፰ ፳፫ ።

፫ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለሙሴ ዛቲ ይእቲ ምድር ዘመሐልኩ ለአብርሃም ወለይስሐቅ ወለያዕቆብ ወእቤሎሙ ለዘርእክሙ እሁባ ወናሁ አርአይኩከሃ ለከ በአዕይንቲከ ፥ ወባሕቱ ህየ ኢትበውእ ።

እግዚአብሔር ሙሴን እንዲህ አለው ፤ ለልጆቻችሁ እሰጣታለሁ ብሎ ለአብርሃም ለይስሐቅና ለያዕቆብ የማልኩላቸው ምድር ይህች ናት ፡ እነሆ ላንተ በዓይኖችህ አሳየሁህ ፤ ነገር ግን ወደዚያ አትገባም ። ዘፍ ፲፪ ፯ ።

፬ ወሞተ ሙሴ ቍልዔሁ ለእግዚአብሔር በምድረ ሞዓብ በቃለ እግዚአብሔር ።

የእግዚአብሔር ባለሟሉ ሙሴም እንደ እግዚአብሔር ቃል በሞዓብ ምድር ሞተ ።

፭ ወቀበርዎ ውስተ ምድረ ናባው ቅሩበ ቤተ ፌጎር ወአልቦ ዘየአምር መኑሂ መቃብሮ እስከ ዛቲ ዕለት ።

በፌጎር (ጣኦት) ቤት አቅራቢያ በምትሆን በሞዓብ ምድር ቀበሩት ፤ ነገር ግን እስከዚች ቀን ድረስ ማንም ማን መቃብሩን የሚያውቅ የለም ። ይሁ ፩ ፱ ።

፮ ምእት ወዕሥራ ዓመቲሁ ሎቱ ለሙሴ አመ ሞተ ፥ ወኢተሐምጋ አዕይንቲሁ ወኢማሰና ።

ሙሴም በሞተ ጊዜ ዕድሜው መቶ ሃያ ዘመን ሁኖት ነበር ፤ ዓይኖቹም አልደፈረሱም አልፈዘዙም ነበር ።

፰ ወበከይዎ ደቂቀ እስራኤል ለሙሴ በአራቦት ዘሞዓብ
በኀበ ዮርዳኖስ ዘመንገለ ኢያሪኮ ሠላሳ መዋዕለ፣ ወተፈ
ጸመ መዋዕለ ላሁ ለሙሴ ዘበከይዎ ።

የእስራኤል ልጆች ለሙሴ የኢያሪኮ አንጻር በምትሆን
በዮርዳኖስ ማዶ ባለች የሞዓብ ክፍል በምትሆን በአራቦት
ሠላሳ ቀን አለቀሱለት፣ ለሙሴ ያለቀሱለትም ወራት አለቀ።

፱ ወኢያሱ ወልደ ነዌ ተመልአ መንፈሰ ጥበብ እስመ
ወደየ እዴሁ ሙሴ ላዕሌሁ ወተአዘዙ ሎቱ ኵሉ ደቂቀ እስ
ራኤል፣ ወገብሩ ኵሎ ዘከመ አዘዘ እግዚአብሔር ለሙሴ ።

ሙሴ በአንብሮተ እጅ ሹሞታልና የነዌ ልጅ ኢያሱም
ጥበብ የሚገልጽ መንፈስ ቅዱስን ተመላ፣ የእስራኤልም
ልጆች ሁሉ ታዘዙለት፣ እግዚአብሔር ሙሴን እንዳዘዘው
ሁሉን አደረጉ። ዘኁ፣ ፳፯ ፲፰፣ ኢሳ፡ ፲፩ ፪ ።

፲ ወኢተንሥአ እንከ ነቢይ ውስተ እስራኤል ዘከመ
ሙሴ ዘተናገሮ እግዚአብሔር ገጸ በገጽ ።

እግዚአብሔር ፊት ለፊት እንደ ተናገረው እንደ ሙሴ
ያለ ነቢይ ከዚያ ወዲህ በእስራኤል ዘንድ አልተነሣም ።

፲፩ ወበኵሉ ተአምር፣ ወመድምም ዘፈነዎ እግዚአብሔር
ከመ ይግበሮ በምድረ ግብጽ ላዕለ ፈርዖን ወላዕለ መገብቱ
ወላዕለ ምድሩ ።

በግብጽ ምድር በመኳንንቱና በፈርዖን በአገሩም ላይ
ያደርገው ዘንድ እግዚአብሔር በላከው ተአምራት ሁሉ
ቃል ለቃል እንደተናገረው ።

፲፪ ዐበይተ መድምመ፣ ወእደ ጽንዕተ፤ ወመዝራዕተ ል
ዑለ ኵሎ ዘገብረ ሙሴ በቅድመ ኵሉ እስራኤል ።

ሙሴ በእስራኤል ፊት ታላላቅ ተአምራት በጸናች
(ዘጠኝ መቅሠፍት) በተዘረጋች ክንድ (ዓሥረኛ ሞተ በኵ
ር፣ ዓሥራ አንደኛ ሥጥመተ ባሕርን) አደረገ።



ተፈጸመ ኦሪት ዘዳግም፣
ወስብሐት ለእግዚአብሔር ጸጋዌ ጸጋ ፍጹም፣
አሜን።



ፍጹም ጸጋን ለሰጠ ለእግዚአብሔር፣
ክብር ምስጋና ይግባውና፣ ሙሴ ዳግመኛ
የተናገረው ነገር ደረሰ ተፈጸመ።

# ኦሪት ዘኢያሱ

ምዕራፍ ፩ ።

፩ ወኮነ እምድኅረ ሞተ ሙሴ ገብረ እግዚአብሔር ፤ ይ
ቤሎ እግዚአብሔር ለኢያሱ ወልደ ነዌ ላእኩ ለሙሴ ።

፪ ናሁ ሞተ ሙሴ ቍልዔየ ወይእዜኒ ተንሥእ ወዕድዎ
ለዝንቱ ዮርዳኖስ አንተ ወኵሉ ዝንቱ ሕዝብ ውስተ ምድ
ር እንተ እሁበክሙ አነ ለክሙ ለደቂቀ እስራኤል ።
፫ ኵሎ መካነ ኀበ ኬዳ እገሪክሙ ለክሙ ነዋ እሁበክሙ
በከመ እቤሎ ለሙሴ ።
፬ እምገዳም ዘአንጢሊባኖን እስከ ፈለግ ዐቢይ ፣ ፈለገ
ኤፍራጥስ ኵሎ ምድሮሙ ለኬጥያውያን ወእስከ ደኃሪት
ባሕር ፣ ወእስከ ምዕራብ ፀሐይ ይኩን ደወልክሙ ።

፭ ወአልቦ ሰብእ ዘይትቃወም ቅድሜከ በኵሉ መዋዕለ
ሕይወትከ ወበከመ ሀሎኩ ምስለ ሙሴ ከማሁ እሄሉ ምስ
ሌከ ወኢየኀድገከ ወኢይትሔወረከ ።
፮ ጽናዕ ወትባዕ እስመ አንተ ትከፍሎሙ ለኵሎሙ ለዝ
ንቱ ሕዝብ ምድረ እንተ መሐልኩ ለአበዊሆሙ ከመ
አሀበሙ ።
፯ ወባሕቱ ጽናዕ ወትባዕ ጥቀ ከመ ትዕቀብ ወትግበር
ኵሎ ሕገ ዘከም አዘዘከ ሙሴ ቍልዔየ ፣ ወኢትትገ
ኃሥ እምኔሁ ኢ ለየማን ወኢ ለፀጋም ከመ ታእምር ኵሎ
ዘከመ ትገብር ።
፰ ወኢትትኀደግ መጽሐፉ ለዝንቱ እምአፉከ ወአንብብ
ቦቱ መዐልተ ወሌሊተ ከመ ታእምር ኵሎ ገቢረ ዘጽሑፍ
ውስቴቱ እስመ ትረትዕ ፍኖትከ ወቦቱ ትጠበብ ።
፱ ወናሁ እኤዝዘከ ትባእ ወጽናዕ ወኢትፍራህ ወኢት
ደንግፅ እስመ ሀለወ እግዚአብሔር አምላክከ ምስሌከ ው
ስተ ኵሉ ዘሖርከ ።
፲ ወአዘዞሙ ኢያሱ ለጸሐፍተ ሕዝብ ወይቤሎሙ ፤ ባኡ
ውስተ ትዕይንት ወአዝዝዎሙ ለሕዝብ ወበልዎሙ አስተ
ዳልዉ ለክሙ ስንቀ ።
፲፩ እስመ እስከ ሠሉስ መዋዕል ተዐድውዎ ለዝንቱ ዮር
ዳኖስ አንትሙ ወትበውኡ ምድረ እንተ ይሁበክሙ እግ
ዚአብሔር አምላከ አበዊክሙ ከመ ትትዋረስዋ ።

፲፪ ወለሮቤልሂ ወለጋድ ወለመንፈቀ ነገደ ምናሴሂ ይቤ
ሎሙ ኢያሱ ፤ ተዘከሩ ቃለ ዘአዘዘክሙ ሙሴ ቍልዔሁ

ምዕራፍ ፩ ።

የእግዚአብሔር አገልጋይ ሙሴ ከሞተ በኋላ እንዲህ
ሆነ የእግዚአብሔር አገልጋይ የሆነ የነዌ ልጅ ኢያሱን
እንዲህ አለው ። ዘፀ ፳፬ ፲፫ ፣ ዘዳ ፩ ፴፰ ።
እነሆ ባለሟሌ ሙሴ ሞተ አሁን ተነሥተህ አንተ ይህንን
ዮርዳኖስ ተሻገረው ለናንተ ለእስራኤል ልጆች ሁሉ እኔ
ወደ ምሰጣችሁ አገር ለመሄድ ይህም ሁሉ ወገን ይሻገረው።
ለሙሴ እንደ ነገርሁት እግሮቻችሁ የረገጡትን ቦታ
ሁሉ እነሆ ለናንተ እሰጣችኋለሁ ። ዘዳ ፲፩ ፳፬ ።
ከአንጢሊባኖን ምድረ በዳ ጀምሮ እስከ ታላቁ ወንዝ
እስከ ኤፍራጥስ ድረስ የኬጥያውያንን አገር ሁሉ እሰጣች
ኋለሁ እስከ ፀሐይ መግቢያ ድረስና እስከ ኋለኛይቱ ባሕር
ድረስ ወሰናችሁ ይሁን ። ዘፍ ፲፫ ፲፭ ፣ ዘፀ ፳፫ ፴፩ ።
በሕይወት በኖርክበት ዘመን ሁሉ በፊትህ የሚከራ
ከር የለም ፣ ከሙሴ ጋር በረድኤት እንደ ኖርሁ ካንተም
ጋራ በረድኤት እኖራለሁ አልለይህም ቸልም አልልህም።
እሰጣቸው ዘንድ ለአባቶቻቸው የማልኩላቸውን ም
ድር አንተ ለነዚህ ወገኖች ትከፍላቸዋለህና ጨክን ፣
በርታ አለው ። ዘዳ ፴፩ ፳ ።
ነገር ግን ባለሟሌ ሙሴ እንዳዘዘህ ሕጉን ሁሉ ጠብ
ቀህ ታደርግ ዘንድ ፈጽመህ በርታ ጨክን ፣ የምታደርገ
ውን ሁሉ ታውቅ ዘንድ ከሱ ወደ ቀኝም ወደ ግራም
አትበል ። ዘዳ ፭ ፴፪ ፣ ኢያ ፲፩ ፲፭ ።
ይህም መጽሐፍ ከአፍህ አይለይ ፣ ሥራህ ትቀናለችና
በሱም አዋቂ ትሆናለህና በሱ የተጻፈውን ሥራ ታውቅ
ዘንድ በመዓልትም በሌሊትም እሱን አንብብ ።
እነሆ አዝሃለሁ በሄድክበት ጐዳና ሁሉ ፈጣሪህ እግ
ዚአብሔር ካንተ ጋራ በረድኤት አለና ጨክን ፣ በርታ ፣
አትፍራ ፣ አትደንግጥ ። ዘዳ ፴፩ ፳ ፣ ኢያ ፩ ፮ ።
ኢያሱም በሕዝቡ ላይ የተሾሙትን ሹማምንት ወደ
ሰፈር ገብታችሁ ለናንተ ስንቅ አዘጋጁ ብላችሁ እዘዙዋ
ቸው አላቸው ።
እስከ ሦስት ቀን ድረስ እናንተ ይህን ዮርዳኖስ ትሻገ
ሩታላችሁ ትወርሷት ዘንድ ያላችሁ ያባቶቻችሁ ፈጣሪ
እግዚአብሔር ወደ ሚሰጣችሁ ምድርም ትገባላችሁ ብሎ
አዘዛቸው ። ኢያ ፫ ፪ ።
ጋድንና ሮቤልን የምናሴን ነገድ እኩሌቶችንም ኢያሱ
እነሆ እግዚአብሔር ይህችን አገር ሰጥቶ እናንተን አሳረፋ

ለእግዚአብሔር ወይቤለክሙ ናሁ አዕረፈክሙ እግዚአብ
ሔር ለክሙ ወወሀበክሙ ዛተ ምድረ።
፲፬ ወይንበራ አንስቲያክሙ ወደቂቅክሙ ወእንስሳክሙ
ውስተ ዛቲ ምድር ዘወሀበክሙ ሙሴ በማዕዶተ ዮርዳኖስ
ወአንትሙሰ ዕድዉ ዮርዳኖስ ቅኑታኒክሙ ቅድመ አኃዊ
ክሙ ኵሉ ጽኑዓኒክሙ፡ ወተቃተሉ ሎሙ እስከ አመ
ያዐርፎሙ እግዚአብሔር አምላክነ ለአኃዊክሙ ከማክሙ።

፲፭ ወይወርሱ እሙንቱኒ ምድሮሙ እንተ ይሁቦሙ እግዚ
አብሔር አምላክነ፡ ወተአትዉ እንከ አሐዱ አሐዱ እም
ኔክሙ ውስተ ርስትክሙ፡ ወትወርስዋ አንትሙ ለዛቲ
ምድር ዘወሀበክሙ ሙሴ ቍልዔሁ ለእግዚአብሔር በማ
ዕዶተ ዮርዳኖስ ዘመንገለ ምሥራቀ ፀሐይ።
፲፮ ወአውሥእዎ ለኢያሱ ወይቤልዎ ንገብር ኵሉ ዘአዘ
ዝከነ፡ ወንሑር መክነ ኀበ ፈነውከነ።
፲፯ ወበከመ ተአዘዝነ ለሙሴ በኵሉ፡ ከማሁ ንትኤዘዝ
ለከኒ፡ ወባሕቱ ምስሌከኒ የሀሉ እግዚአብሔር በከመ
ሀለወ ምስለ ሙሴ።
፲፰ ወብእሲ ዘኢተአዘዘ ለከ ወዘክሕደከ ወዘኢሰምዐ ቃ
ለከ ዘአዘዝኮሙ ለይሙት፡ ወይእዜኒ ጽናዕ ወትባዕ።

## ምዕራፍ ፪።

፩ ወፈነወ ኢያሱ እምሰጢን ክልኤተ ወራዙተ ሰብአ
ዐይን ጽሚተ ወይቤሎሙ ዕርጉ ወረአይዋ ለይእቲ ምድር
ወለኢያሪኮኒ።
፪ ወሖሩ እልክቱ ክልኤቱ ወራዙት ወበጽሑ ኢያሪኮ
ወቦኡ ውስተ ቤተ አሐቲ ብእሲት ዘማ እንተ ስማ ራኣብ
ወኀደሩ ህየ።
፫ ወአይድዕዎ ለንጉሠ ኢያሪኮ ወይቤልዎ ቦኡ ዝየ አደ
ው በሌሊት እምደቂቀ እስራኤል ሰብአ ዐይን ከመ ይር
አዩ ብሔረነ።
፬ ወለአከ ንጉሠ ኢያሪኮ ኀበ ራኣብ ወይቤ በልዋ ለራ
ኣብ፡ አውፅኢ እደወ እለ ቦኡ ኀቤኪ ሰብአ ዐይን እሙ
ንቱ ወከመ ይርአዩ ብሔረነ መጽኡ።
፭ ወነሥአቶሙ ይእቲ ብእሲት ለእልክቱ እደው ወኀብ
አቶሙ ወትቤ እደውሰ ቦኡ ኀቤየ ወኢያአመርኩ እም
አይቴ እሙንቱ።
፮ ወእንዘ ዕፅው ኆኅት ወበጽልመት ወፅኡ ውእቶሙ
እደው ወኢያአመርኩ አይቴ እንከ ሖሩ፡ ወሖሩ እንከ
ፍጡነ ትልውዎሙ ወዴግንዎሙ ዮጊ ትረክብዎሙ።
፯ ወይእቲሰ አዕረገቶሙ ውስተ ናሕስ ወኀብአቶሙ
ማእከለ ዕፀው ውስተ ሕለት ዘወጡሕ።
፰ ወዴገንዎሙ ውእቶሙ እደው እንበለ ይቢቱ፡ ወይ
እተ ጊዜ ዐርገት ኀቤሆሙ ውስተ ናሕስ፡ ወትቤሎሙ
አአምር ከመ አግብአ እግዚአብሔር ለብሔር ለክሙ።
፱ እስመ አምጽአ እግዚአብሔር ፍርሀተክሙ ላዕሌነ ወተ
መንሰዉ ኵሎሙ እለ ይነብሩ ውስተ ብሔር እምኔክሙ።
፲ እስመ ሰማዕነ ከመ አይበሳ እግዚአብሔር ለባሕረ ኤር
ትራ እምቅድመ ገጽክሙ አመ አውፅአክሙ እምድረ ግብ

ችሁ ብሎ የእግዚአብሔር ባለሟል ሙሴ ያዘዛችሁን ቃል
አስታውሱ። ዘኍ፡ ፴፪ ፳-፳፰።
ሚስቶቻችሁ፣ ልጆቻችሁና ከብቶቻችሁ ሙሴ በዮር
ዳኖስ ወድያ ማዶ በሰጣችሁ በዚች አገር ይቀመጡ፤ እና
ንተ ግን እፉ-እፉችሁን ታጥቃችሁ አርበኞቻችሁ ሁሉ
ፈጣሪያችሁ እግዚአብሔር እንደናንተ እስኪያሳርፋቸው
ድረስ በወንድሞቻችሁ ፊት ዮርዳኖስን ተሻግራችሁ
ተዋጉዋቸው።
እነሱቸውም ፈጣሪያችን እግዚአብሔር የሚሰጣችሁን
ምድራቸውን ይወርሱ ከዚህ በኋላ ከናንተ አንዱም አን
ዱም ወደ ርስታችሁ ትመለሳላችሁ፤ እናንተም የእግዚአ
ብሔር ባለሟል ሙሴ በፀሐይ መውጫ በኩል በዮርዳኖስ
ማዶ የሰጣችሁ ይህችን ምድር ትወርሷታላችሁ አላቸው።
እነሱም ያዘዝከንን ሁሉ እናደርጋለን ወዳልክንም ቦታ
እንሄዳለን ብለው መለሱለት።
ለሙሴ በሁሉ እንደታዘዝን ላንተም እንደሱ እንታዘ
ዛለን ብቻ እግዚአብሔር ከሙሴ ጋር በረድኤት እንደኖረ
ከንተም ጋራ በረድኤት ይኑር። ኢያ፡ ፩ ፭።
ላንተ ያልተዘዘ አንተን ክዶ ያዘዝከውን ቃል ያልሰማ
ሰው ይሙት፤ አሁንም ጨክን በርታ።

## ምዕራፍ ፪።

ኢያሱ ሁለቱን ጒብኞች ሰውሮ ከሰጢን ልኮ ወጥ
ታችሁ ያችን ምድር እዩዋት ኢያሪኮንም እዩዋት አላ
ቸው።
እነዚያም ሁለት ጐልማሶች ሂደው ኢያሪኮ ደርሰው
ስሟ ራኣብ ወደምትባል ወደ አንዲት ዘማ ሴት ቤት ገብ
ተው በዚያ አደሩ። ኢያ፡ ፩ ፲፩፡ ፫ ፪፡ ማቴ፡ ፩ ፭።
አገራችንን ያዩ ዘንድ ከእስራኤል ልጆች ጒብኝዎች
ሰዎች እነሆ በሌሊት ገቡ ብለው ለኢያሪኮ ንጉሥ ነገሩት።

የኢያሪኮም ንጉሥ ዘማ ወደምትሆን ወደ ራኣብ ልኮ
ራኣብን አገራችንን ያዩ ዘንድ መጥተው ከንቺ ዘንድ የገቡ
እነዚያን ጒብኝዎች ሰዎች አውጪ በሏት አለ።
ያችም ሴት እነዚያን ሁለቱን ጐልማሶች ወስዳ ሠወረ
ቻቸው፤ ሰዎች ከኔ ዘንድ ገብተው ነበር፤ ነገር ግን ወዴ
ት እንደ ሄዱ አላወቅሁም። ፪ ሳሙ፡ ፲፯ ፲፱።
ደጃፉ ተዘግቶ ሳለ እነዚያ ሰዎች በጨለማ ወጡ፤ ወ
ዴት እንደ ሄዱም አላውቅሁም፤ ፈጥናችሁ ሂዱችሁ ተከ
ተሏቸው ወይ ታገኙዋቸው ይሆናል አለቻቸው።
እሷ ግን ወደ ሰገነት አውጥታ በተከመረ ዕንጨት
መካከል በቀርቀሃ ጠቅልላ አቆመቻቸው።
እነዚያም ሰዎች ሳያድሩ ተከሏቸው፤ ያን ጊዜ ወደነ
ሳቸው ወደ ሰገነት ወጥታ እግዚአብሔር አገሪቱን ለናንተ
አሳልፎ እንደ ሰጣት አውቃለሁ።
መፈራታችሁን በኛ ላይ አምጥቶ ብናልና ከናንተ ፊት
የ ተነሣም በአገር የሚኖሩ ሰዎች እንደ ሰም ቀልጠዋልና።
ከግብጽ ምድር በወጣችሁ ጊዜ ከፊታችሁ የኤርትራን
ባሕር እግዚአብሔር እንዳደረቀላችሁ በዮርዳኖስ ማዶም

ጽ ወኵሎ ዘገብረ ላዕለ ነገሥተ አሞሬዎን እለ ሀለዉ ማዕዶተ ዮርዳኖስ ለሴዎን ወለዖግ እለ ሠረውክምዎሙ ።

ባሉ ነገሥታት በጠፋችኋቸው በዖግና በሴዎን ላይ ያደረገውን ሁሉ ስለ ሰማን ለናንተ አሳልፎ እንደ ሰጣት አውቃለሁ አለቻቸው ። ዘፀ፡ ፲፭ ፲፮፡ ፳፫ ፳፬ ።

፲፩ ወሰበ ሰማዕነ ንሕነ ደንገፅነ በልብነ ወኢተርፈ ነፍስ አሐዱ እምኔነ እምቅድመ ገጽክሙ እስመ እግዚአብሔር አምላክክሙ ውእቱ አምላክ በሰማይ በላዕሉ ወበምድር በታሕቱ ።

እኛም በሰማን ጊዜ ልቡናችን ደነገጠ፤ ከፊታችሁም የተነሣ ከኛ ያንዱ ሰውነት ስንኳ ሳትደነግጥ አልቀረችም ፈጣሪያችሁ እግዚአብሔር ከምድር በላይ ባለ በሰማይ ከሰማይ በታች ባለ በምድር ፈጣሪ ነውና ።

፲፪ ወይእዜኒ መሐሉ ሊተ በእግዚአብሔር በከመ ገበርኩ ምስሌክሙ ምሕረተ ከመ ትግበሩ ምስሌየ ምሕረተ ወምስለ ቤተ አቡየ ወተሀቡኒ ተአምረ በጽድቅ ።

አሁንም ለናንተ በጎ እንዳደረግሁላችሁ ለኔም ላባቴም ወገን በጎ ታደርጉልኝ ዘንድ በእግዚአብሔር ማሉልኝ፤ በእውነትም ምልክት ስጡኝ ። ዘፀ፡ ፲፭ ፲፬ ።

፲፫ ወአሕይዉ ቤተ አቡየ ወእምየ ወአኀውየ ወኵሎ ቤትየ ወኵሎ ዘዚአሆሙ ወአድኅኑ ነፍስነ እሞት ።

የናቴንና ያባቴን ወገን ወንድሞቼንም ወገኔንም ሁሉ ወገናቸውንም ሁሉ አድኑ፤ ሰውነታችንም ከሞት አድኑ አለቻቸው ።

፲፬ ወይቤልዋ እሙንቱ አደው ነፍስነ ህየንቴክሙ ውስተ ሞት ።

እነዚያም ሰዎች ሰውነታችንን ስለናንተ ለሞት አሳልፈን እንሰጣለን አሏት ።

፲፭ ወትቤሎሙ ይእቲ አመ አግብአ እግዚአብሔር ለሀገርነ ውስተ እደዊክሙ ግበሩ ምስሌየ ምሕረተ ወጽድቀ ።

ያችም ሴት እግዚአብሔር አገራችንን በእጃችሁ ከጣላት ለኔ ቸርነትንና ይቅርታን አድርጉልኝ አለቻቸው ።

፲፮ ወይቤልዋ እሙንቱ አደው ለእመ ኢያይዳዕኪ በእንቲአነ ንገብር ምሕረተ ምስሌኪ ለእመ አግብአ እግዚአብሔር ለሀገርክሙ ለነ በጽድቅ ።

እነዚያም ሰዎች እግዚአብሔር በእውነት አገራችሁን በእጃችን ከጣለልን የኛን ነገር (ምሥጢር) ካላወጣሽ ቸርነት እናደርግልሻለን አሏት ። መሳ፡ ፩ ፳፬ ።

፲፯ ወአውረደቶሙ በሐብል እንተ መስኮት እስመ ቤታ በጥቅም ውእቱ ወትነብር ይእቲ ውስተ ሀረፍት ።

ቤቷ በቅጥር አጠገብ ነውና፤ እርሷም በቅጥር አጠገብ ትኖራለችና ከመስኮቱ በገመድ አወረደቻቸው ።

፲፰ ወትቤሎሙ ሑሩ እንተ ደብር ከመ ኢይርከቡክሙ እለ ይዴግኑክሙ ወተኀብኡ ህየ ሠሉሰ መዋዕለ እስከ ይገብኡ እለ ይዴግኑክሙ ወእምዝ ትገብኡ ውስተ ፍኖትክሙ ።

የተከተሏችሁ ሰዎች እንዳያገኟችሁ ደጋ ደጋውን ሂዱ፤ የተከተሏችሁም ሰዎች እስኪመለሱ ድረስ ሦስት ቀን በዚያ ተሠወሩ፤ ከዚያ በኋላ ወደ ጐዳናችሁ ትመለሳላችሁ አለቻቸው ።

፲፱ ወይቤልዋ እሙንቱ አደው፤ ንጹሓን ንሕነ እመሐላኪ ዘአምሐልክነ ።

እነዚያም ሰዎች እኛን ከማልሽልን መሐላ ንጹሐን ነን፤ አሉዋት ። ዘፀ፡ ፳ ፯፡ ኢያ፡ ፯ ፳፫ ።

፳ ናሁ ንሕነ ንበውእ ውስተ ጽንፈ ሀገር ወደዪ ዘንተ ፈትለ ቀይሐ ዘለይ ውስተ መስኮት እንተ ባቲ አውረድክነ ወአበኪኒ ወእመኪኒ ወአኀዊኪኒ አስተጋብኢ ኀቤኪ ውስተ ቤትኪ ።

እነሆ እኛ ወደ አገር ዳርቻ እንገባለን ይህን የቀይ ሐር ፈትል እኛን ባወረድሽበት መስኮት አድርጊ (እሰሪ) እናትሽንና አባትሽን ወንድሞችሽንም ከንቺ ዘንድ በቤትሽ ሰብስቢ ። ዘፍ፡ ፴፰ ፳፰፡ ኢያ፡ ፪ ፲፪ ።

፳፩ ወኵሉ ዘወፅአ አፍአ እምነ ኆኅተ ቤትኪ ይመውት፤ ወንሕነሰ ንጹሓን ንሕነ እምዝንቱ መሐላ ዘአምሐልክነ ወበሕቱ ኵሉ ዘሀለወ ምስሌኪ ውስተ ቤትኪ ለእመ ሞተ ላዕሌነ ኀጢአት ።

ከቤትሽ ደጃፍ ወደ ውጪ የወጣው ሁሉ ይሞታል፤ እኛ ከዚህ ከማልሽን መሐላ ንጹሐን ነን፤ ካንቺ ጋራ በቤትሽ ያለው ሁሉ ቢሞት ግን በኛ ዕዳ ይሆንብናል ።

፳፪ ወለእመሰ ከሠትኪ ነገረነ ንጹሓን ንሕነ እምዝንቱ መሐላኪ፤ ወትቤሎሙ ይኩን በከመ ትቤሉ ።

ነገራችንን (ምሥጢራችንን) ብታወጪ ግን ከዚህ ከመሐላሽ ንጹሐን ነን፤ እንዳላችሁም ይሁን አለቻቸው ።

፳፫ ወፈነወቶሙ ወሖሩ ወአሰረት ዝክተ ፈትለ ዘለይ በመስኮት፤ ወወዕኡ ወሖሩ ውስተ ደብር ።

ሸኘቻቸውም ሄዱ፤ ያንንም ቀይ ሐር በመስኮት አሰረች፤ እነሱም ወጥተው ደጋደጋውን ሄዱ ።

፳፬ ወነበሩ ህየ ሠሉሰ መዋዕለ እስከ ገብኡ እለ ዴገንዎሙ ወኀሠሥዎሙ ወኢረከብዎሙ ውስተ ፍኖዋት ።

የተከሉዋቸውም ሰዎች እስኪመለሱ ድረስ ሦስት ቀን በዚያ አደሩ፤ አሳዳጆቹ በመንገዶቹ ፈልገው አጥተዋቸው ተመለሱ ።

፳፭ ወገብኡ እልክቱ አደው ወወረዱ እምደብር ወኀለፉ ወበጽሑ ኀበ ኢያሱ ወልደ ነዌ ወዜነውዎ ኵሎ ዘገብሩ ።

ከዚህ በኋላ እነኛ ሰዎች ከተራራው ወርደው ሄዱ፤ ከነዌ ልጅ ኢያሱም ዘንድ ደርሰው ያደረጉትን ሁሉ ነገሩት ።

፳፮ ወይቤልዎ አግብአ እግዚአብሔር ኵሎ ምድረ ውስተ እዴነ ወደንገፁ ኵሎሙ አሕዛብ እለ ይነብሩ ውስተ ይእቲ ምድር እምኔነ ።

እግዚአብሔር አገሩን ሁሉ በእጃችን ጣለልን፤ በዚያች አገር የሚኖሩ አሕዛብም ሁሉ ከኛ የተነሣ ደነገጡ አሉት ። ኢያ፡ ፯ ፱፡ ፰ ፩ ።

## ምዕራፍ ፫ ።

፩ ወጌሠ በጽባሕ ኢያሱ ወግዕዙ እምሰጢን ወበጽሑ ዮርዳኖስ ፡ ውእቱ ወኵሉ እስራኤል ወኀደሩ ህየ እንበለ ይዕድዉ ።

፪ ወእምድኅረ ሠለስ መዋዕል በኡ ጸሐፍት ማእከለ ትዕይንት ፡ ወአስተኀለፉ ለሕዝብ ።

፫ ወይቤልዎሙ እምከመ ርኢክሙ ታቦተ ሕጉ ለእግዚአብሔር አምላክነ ወካህናቲነ ወሌዋውያኒነ እንዘ ይፀውርዋ ግዕዙ አንትሙኒ እመካናቲክሙ ወትልዉ ድኅሬሃ ።

፬ ወበሕቁ ርኁቀ ይኩን ማእከሌክሙ ወማእከሌሃ መጠነ ዕሥራ ምእት በእመት ወበመስፈርቱ ቁሙ ወኢትቅረብዋ ከመ ታእምሩ ፍኖተ እንተ ተሐውሩ እስመ ኢሖርክምዋ ለይእቲ ፍኖት ትካት ።

፭ ወይቤሎሙ ኢያሱ ለሕዝብ አንጽሑ ርእሰክሙ ለጌሠም እስመ ጌሠመ ይገብር እግዚአብሔር መድምመ ለክሙ ።

፮ ወይቤሎሙ ኢያሱ ለካህናት ንሥኡ ታቦተ ሕጉ ለእግዚአብሔር ወሑሩ ቅድመ ሕዝብ ፡ ወነሥኡ ካህናት ታቦተ ሕጉ ለእግዚአብሔር ወሖሩ ቅድመ ሕዝብ ።

፯ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለኢያሱ ናሁ በዛቲ ዕለት እአኀዝ አዕቢዮ በቅድመ ኵሉ ደቂቀ እስራኤል ከመ ያእምሩ ከመ ሀሎኩ ምስሌሁ በከመ ሀሎኩ ምስለ ሙሴ ።

፰ ወይእዜኒ አዝዞሙ ለካህናት እለ ይፀውሩ ታቦተ ወበ ሎሙ እምከመ በአክሙ ውስተ ጽንፈ ማዩ ለዮርዳኖስ ቁሙ ውስቴቱ ።

፱ ወይቤሎሙ ኢያሱ ለደቂቀ እስራኤል ቅረቡ ዝየ ወስምዑ ቃለ እግዚአብሔር አምላክነ ።

፲ ወይቤሎሙ ኢያሱ በዝንቱ ተአምሩ ከመ ሕያው ውእቱ እግዚአብሔር ዘምስሌክሙ ወአጥፍኦ ያጠፍኦሙ እምቅድመ ገጽክሙ ለከናኔዎን ወለኬጤዎን ወለፌሬዜዎን ወለኤዌዎን ወለአሞሬዎን ወለኢያቡሴዎን ወለጌርጌሴዎን ።

፲፩ ወናሁ ታቦተ ሕጉ ለእግዚአብሔር እግዚአ ኵሉ ምድር ተዐዱ ቅድሜክሙ ዮርዳኖስ ።

፲፪ ወኅረዩ ለክሙ ዐሠርተ ወክልኤተ አደወ እምደቂቀ እስራኤል አሐደ አሐደ ብእሴ እምአሐዱ አሐዱ ነገድ ።

፲፫ ወሰበ አቀሙ እገሪሆሙ ካህናት እለ ይፀውሩ ታቦተ ሕጉ ለእግዚአብሔር ውስተ ማየ ዮርዳኖስ ይነጽፍ ማየ ዮርዳኖስ ወማይኒ ዘይወርድ እምላዕሉ ይቀውም ።

፲፬ ወእምዝ ሰበግዕዙ ሕዝብ እማኅደሪሆሙ ከመ ይዕድውዋ ለዮርዳኖስ ወካህናትኒ ፆሩ ታቦተ ሕጉ ለእግዚአብሔር ወሖሩ ቅድመ ሕዝብ ።

፲፭ ወሰበ በኡ ካህናት እለ ይፀውሩ ታቦተ ሕጉ ለእግዚአብሔር ውስተ ዮርዳኖስ ወተጠምቃ እገሪሆሙ ለካህናት እለ ይፀውሩ ታቦተ ሕግ ውስተ ጽንፉ ለዮርዳኖስ ወምሉእ ውእቱ ዮርዳኖስ እስከ ድንጋጊሁ ከመ መዋዕለ ክረምት ወከመ አመ ይሠዊ ሥርናይ ።

## ምዕራፍ ፫ ።

ኢያሱ ሲነጋ ገሥግሦ እሱና የእስራኤልም ልጆች ከሰጢን ተጕዘው ዮርዳኖስ ደረሱ ፡ ሳይሻገሩም በዚያ አደሩ ።

ከሦስትም ቀን በኋላ ጸሐፍቶቹ ከሰፈር ማኸል ገብ ተው ለሕዝቡ አዋጅ ነገሩ ። ኢያ፡ ፩ ፲፩ ።

የፈጣሪያችን የእግዚአብሔር የሕጉን ማደሪያ ታቦትን ተሸክመዋቸ ሌዋውያንና ካህናትን ካያችሁ በኋላ እናን ተም ከበታችሁ ተነሥታችሁ አዟን ተከትላችሁ ተጓዙ ።

ነገር ግን በዚና በናንተ መካከል ሃያ ክንድ ያህል የራ ቀ ይሁን በመጠኑ ቁሙ ፡ ያችን መንገድ ቀድሞ አልሄ ዳችሁበትምና የምትሄዱበትን ጐዳና ታውቁ ዘንድ አት ቅረቧት ። ዘዐ፡ ፲፱ ፲፪ ፡ ኢያ፡ ፬ ፲፰ ።

ኢያሱም እግዚአብሔር ለናንተ ነገ ድንቅ ነገር ያደ ርግላችኋልና ፡ ሕዝቡን ለነገ ራሳችሁን (ከኃጢአት) አንጹ አላቸው ። ዘሌ፡ ፳ ፯ ፡ ኢያ፡ ፯ ፲፱ ።

ኢያሱም ካህናቱን የእግዚአብሔርን የሕጉን ማደሪያ ታቦትን ይዛችሁ በሕዝቡ ፊት ሂዱ አላቸው ፡ የሕጉንም ማደሪያ ታቦት ይዘው በሕዝቡ ፊት አለፉ ።

እግዚአብሔር ኢያሱን እንዲህ አለው ፤ ከሙሴ ጋር በረድኤት እንደኖርሁ ካንተም ጋር በረድኤት እንዳለሁ ያውቁ ዘንድ እነሆ በዚች ቀን በእስራኤል ፊት ሁሉ አከ ብርህ አገንህ ዘንድ እጀምራለሁ ። ኢያ፡ ፬ ፲፬ ።

አሁንም ታቦቲቱን የሚሸከሙ ካህናትን ወደ ዮርዳ ኖስ ዳርቻ በገባችሁ ጊዜ በውስጡ ቁሙ ብለህ እዘዛቸው አለው ። ኢያ፡ ፫ ፫ ፡ ፫ ፲፯ ።

ኢያሱም የእስራኤልን ልጆች ወደዚህ ቅረቡ የፈጣሪያችን የእግዚአብሔርን ቃል ስሙ አላቸው ።

ኢያሱ ከናንተ ጋራ በረድኤት ጸንቶ የሚኖር እግዚ አብሔር ሕያው እንደሆነ በዚህ ታውቃላችሁ ኬጤዎንን ከናኔዎንን ፌርዜዎንን ኤዌዎንን ኢያቡሴዎንን አሞሬዎን ንና ጌርጌሴዎንን ከፊታችሁ ፈጽሞ ያጠፋቸዋል ።

የዓለሙ ሁሉ ጌታ የእግዚአብሔር የሕጉ ማደሪያ ታቦ ትም እነሆ በፊታችሁ ዮርዳኖስን ትሻገራለች ።

ከእስራኤል ልጆች ከአንዳንዱ ነገድ አንድ አንድ ሰው ዓሥራ ሁለት ሰዎች ምረጡ አላቸው ። ዘኍ፡ ፲፫ ፪ ።

የእግዚአብሔር ሕግ ማደሪያ ታቦትን የሚሸከሙ ካህ ናት በዮርዳኖስ እግራቸውን ውኃ መካከል ብቆሙ ጊዜ የዮርዳኖስ ውኃ ይደርቃል ፡ ከላይ የሚወርደውም ውኃ ይቆማል አላቸው ። ዘፀ፡ ፲፭ ፲፰ ፡ ኢያ፡ ፫ ፲፭ ።

ከዚህ በኋላ ዮርዳኖስን ይሻገሩት ዘንድ በተጓዙ ጊዜ ካህናቱም የእግዚአብሔር የሕጉን ማደሪያ ታቦትን ተሸክ መው በሄዱ ጊዜ ። ግብ፡ ሐዋ፡ ፯ ፵፭ ።

የእግዚአብሔር የሕጉን ማደሪያ ታቦትን የሚሸከሙ ካህናት ወደ ዮርዳኖስ በገቡ ጊዜ የሕጉ ማደሪያ ታቦትን የሚሸከሙ የካህናቱ እግሮቻቸውም በተጠመቁ ጊዜ ዮርዳኖስ እንደ ክረምት ወራት ሥንዴም እንደ ሚሸት በት ወራት እስከ ዳርቻው ድረስ መልቶ ነበር ።

፲፮ ወቆመ ማይ ዘይወርድ እምላዕሉ ወቆመ ከመ አረፍት እንዘ ይርኅቅ ቀዊመ ጥቀ እስከ ደወለ ቀርያታርም ወዘይወርድ ወረደ ውስተ ባሕር ወእስከ ባሕረ ኤሎን ነጽፈ ወየብሰ ወቆሙ ሕዝብ አንጻረ ኢያሪኮ ።

ከላይ የሚወርደው ውኃ እስከ ቀርያታርም አውራጃ ድረስ ርቆ እንደ ግድግዳ ቆመ ፣ የሚወርደውም ውኃ ወደ ባሕር ወረደ ፣ እስከ ባሕረ ጨውም ድረስ ፈጽሞ ደረቀ ፣ ሕዝቡም በኢያሪኮ አንጻር ቆሙ ። ፩ ነገ፡ ፬ ፲፪ ።

፲፯ ወከህናት እለ ይፀውሩ ታቦተ ሕጉ ለእግዚአብሔር ቆሙ ውስተ ይቡስ ማእከለ ዮርዳኖስ ርሡያኒሆሙ ወኵሉ ደቂቀ እስራኤል ዐደዉ እንተ ማእከለ የብስ እስከ ተገምሩ ኵሉ ሕዝብ ወዐደዉ ዮርዳኖስ ።

የእግዚአብሔር የሕጉ ማደሪያ ታቦትን የሚሸከሙ ካህናትም አጊጠው በዮርዳኖስ መካከል በደረቅ ቆሙ ፣ ሕዝቡም ሁሉ አክተው እስኪሻገሩ ድረስ ደርሰው የእስራኤል ልጆች ሁሉ በደረቅ ተሻገሩ ዮርዳኖስንም ተሻገሩ።

## ምዕራፍ ፬ ።

፩ ወሰበ ተገምሩ ኵሉ ሕዝብ ወዐደዉ ዮርዳኖስ ይቤሎ እግዚአብሔር ለኢያሱ ንሣእ ዐሠርተ ወክልኤተ እደወ አሐደ አሐደ ብእሴ እምአሐዱ አሐዱ ነገድ ።

ሕዝቡ ሁሉ ዮርዳኖስን ፈጽመው በተሻገሩ ጊዜ እግዚአብሔር ኢያሱን እንዲህ አለው ፤ ከነዳንዱ ነገድ አንዳንድ ሰው መርጠህ ዓሥራ ሁለት ሰዎች አቅርብ ።

፪ ወአዝዞሙ ከመ ይንሥኡ ሎሙ እምዝየ እማእከለ ዮርዳኖስ እምኀበ ቆማ እገሪሆሙ ለካህናት ዐሠርተ ወክልኤተ እእባነ ከዋዋተ ወንሥእዎን ምስሌክሙ ወዕቀብዎን በበነገድክሙ ኀበ ኀደርክሙ ህየ በሌሊት ።

የካህናቱ እግሮች ከቆሙበት ከዚያ ከዮርዳኖስ እንክብል እንክብል የሆኑ ደንጊያዎችን ለነሱ ያመጡ ዘንድ እዘዛቸው ፣ ከናንተም ጋር ይዛችኋቸው ሂዱ ፣ ሌሊት በደራችሁበት በዚያ በየነገዳችሁ ጠብቋቸው ።

፫ ወጸውዐ ኢያሱ ዐሠርተ ወክልኤተ እደወ እምክቡራኒሆሙ ለደቂቀ እስራኤል ፣ አሐደ አሐደ ብእሴ እምአሐዱ አሐዱ ነገድ ።

ኢያሱም ከእስራኤል ልጆች ሹማምንት ከነዳንድ ነገድ አንዳንድ ሰው መርጦ ዓሥራ ሁለት ሰዎችን ጠራ ። ዘኍ፡ ፲፫ ፪ ። ዘዳ፡ ፩ ፳፫ ።

፬ ወይቤሎሙ ንዑ ወእምጽኡ ቅድሜየ ወቅድመ እግዚአብሔር እማእከለ ዮርዳኖስ ወንሥኡ እምዝየ አሐተ አሐተ እብነ ።

ከዚህ ከዮርዳኖስ መካከል አንዳንድ ደንጊያ አንሥታችሁ ወደ እግዚአብሔርና ወደኔ አምጡ ። ኢያ፡ ፩ ፬ ፣ ፲፭ ። ፩ ነገ፡ ፲፰ ፴፩ ።

፭ ወፁሩ ውስተ መታክፍቲክሙ በከመ ኊላቌሆሙ ለዐሠርቱ ወክልኤቱ ነገደ እስራኤል ፣ ከመ ይኩንክሙ ተአምረ ወይንበርክሙ ለዝሉፉ ።

ምልክት ይሆኗችሁ ዘንድ ለዘለዓለሙም ይኖሩላችሁ ዘንድ በዓሥራ ሁለቱ ነገደ እስራኤል ቍጥር በጫንቃችሁ ተሸከሙ ። ዘፀ፡ ፲፪ ፳፮ ፣ ኢያ፡ ፬ ፳፩ ።

፮ ከመ ሰበ ተስእለከ ወልድከ ጌሠመ ወይቤለከ ምንትእማንቱ እላንቱ እእባን ፣ ንግሮ አንተ ለወልድከ ወበሎ ፣ እስመ ነጽፈ ዮርዳኖስ ተከዚ እምቅድመ ታቦተ ሕጉ ለእግዚአብሔር እንዘ ነዐዱ ።

ልጅህ ነገ እነዚህ ደንጊያዎች ምንድር ናቸው ፤ ብሎ ቢጠይቅህ ፡ ስንሻገር የዮርዳኖስ ፈሳሽ ከእግዚአብሔር ከሕጉ ማደሪያ ከታቦት ፊት ደርቋልና ስለዚህ ነው ብለህ አንተ ለልጅህ ንገረው ።

፯ ወይኩናክሙ እላንቱ እእባን ተዝካረ ለክሙ ለደቂቀ እስራኤል እስከ ለዓለም ።

እነዚያም ደንጊያዎች ለናንተ ለእስራኤል ልጆች እስከ ዘለዓለም መታሰቢያ ይሁኑዋችሁ አላቸው ።

፰ ወገብሩ ከማሁ ደቂቀ እስራኤል በከመ አዘዞሙ ኢያሱ ወነሥኡ ዐሠርተ ወክልኤተ እእባነ እማእከለ ዮርዳኖስ በከመ አዘዘ እግዚአብሔር ለኢያሱ ወሰበ ተገምሩ ዐዲወ ደቂቀ እስራኤል ተፀቀብዎን ምስሌሆሙ ውስተ ተዓይኒሆሙ ወሤምዎን በህየ ።

የእስራኤልም ልጆች ኢያሱ እንዳዘዛቸው እንዲሁ አደረጉ ፣ የእስራኤል ልጆች አክተው በተሻገሩ ጊዜ እግዚአብሔር ኢያሱን እንዳዘዘው ከዮርዳኖስ መካከል ዓሥራ ሁለት ደንጊያዎችን አመጡ ፣ ከነሱም ጋር በሰፈራቸው ጠበቋቸው በዚያም አኖሩዋቸው ።

፱ ወአቀመ በህየ ኢያሱ ክልአተ እእባነ ዐሠርተ ወክልኤተ ውስተ ዮርዳኖስ ውስተ ውእቱ መካን ኀበ ቆማ እገሪሆሙ ለካህናት እለ ይፀውሩ ታቦተ ሕግ ወሀለዉ ህየ እስከ ዮም ወእስከ ዛቲ ዕለት ።

ኢያሱም የሕጉን ታቦት የሚሸከሙ የካህናቱ እግሮች በቆሙበት በዚያ በዮርዳኖስ መካከል ሌሎች ዓሥራ ሁለት ደንጊያዎችን አቆመ ፣ እስከሁንም ድረስ እስከዚህችም ቀን በዚያ አሉ ።

፲ ወቆሙ ካህናት እለ ይፀውሩ ታቦተ ሕግ ማእከለ ዮርዳኖስ እስከ ፈጸመ ኢያሱ ኵሎ ዘአዘዞ እግዚአብሔር ከመ ይንግሮሙ ለሕዝብ ወአፍጠኑ ዐዲወ ሕዝብ ።

የሕጉን ታቦት የተሸከሙ ካህናትም ኢያሱ ለሕዝቡ ይነግራቸው ዘንድ እግዚአብሔር ያዘዘውን እስኪጨርስ ድረስ በዮርዳኖስ መካከል ቆመው ነበር ሕዝቡም ፈጥነው ተሻገሩ።

፲፩ ወሰበ ተገምሩ ዐዲወ ሕዝብ ዐደወት ታቦተ ሕግ ወእልክቱ እእባን እለ ቅድሜሆሙ ።

ሕዝቡም አክተው በተሻገሩ ጊዜ የሕጉም ታቦት ተሻገረች በፊታቸው ያሉ እኒያ ደንጊያዎችም ተሻገሩ ።

፲፪ ወዐደዉ ደቂቀ ሮቤል ወደቂቀ ጋድ ወመንፈቀ ነገደ ምናሴ ርሡያኒሆሙ ቅድመ ደቂቀ እስራኤል በከመ አዘዞሙ ሙሴ ።

የጋድና የሮቤል ልጆች የነገደ ምናሴም እኩሌቶች ተሰልፈው ሙሴ እንዳዘዛቸው በእስራኤል ልጆች ፊት ተሻገሩ ። ዘፀ፡ ፲፫ ፲፰ ፣ ኢያ፡ ፩ ፲፬ ።

፲፫ አርባዓ ምእት ቅኑታኒሆሙ ለቀትል በደዉ ቅድመ እግዚአብሔር ከመ ይትቃተልዋ ለኢያሪኮ ሀገር።

፲፬ ወበይእቲ ዕለት አዕበዮ እግዚአብሔር ለኢያሱ በቅድመ ኵሉ ደቂቀ እስራኤል ወፈርህዎ ከመ ሙሴ እምጣነ ሕያው ውእቱ።

፲፭ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለኢያሱ፣ እዝዞሙ ለካህናት እለ ይፀውሩ ታቦተ ከመ ይዕርጉ እማእከለ ዮርዳኖስ።

፲፮ ወአዘዞሙ ኢያሱ ለካህናት ወይቤሎሙ ዕርጉ እምዮርዳኖስ።

፲፯ ወከነ ሶበ ወፅኡ ካህናት እለ ይፀውሩ ታቦተ ሕጉ ለእግዚአብሔር እማእከለ ዮርዳኖስ ወኬዱ በእገሪሆሙ ውስተ ምድር ሮጸ ማየ ዮርዳኖስ ወገብአ ውስተ መካናቲሁ ወሖረ ከመ ትካት ወበጽሐ እስከ ድንጋጌሁ።

፲፰ ወእመ ፀሙሩ ለሠርቀ ቀዳሚ ወርኅ ወፅኡ ሕዝብ እምዮርዳኖስ ወግዕዙ ውስተ ገልገላ መንገለ ሠርቀ ፀሐይ እምኢያሪኮ።

፲፱ ወአቀሞን ኢያሱ ለእማንቱ አእባን ፀሠርቱ ወክልኤቱ ውስተ ገልገላ።

፳ ወይቤሎሙ ኢያሱ ለደቂቀ እስራኤል ሶበ ተስእሉክሙ ደቂቅክሙ ወይቤሉክሙ ምንትኑ እላንቱ አእባን፣ ዜንውዎሙ ለደቂቅክሙ ወበልዎሙ እስመ ከመ የብስ ዐደውናሁ ለዝንቱ ዮርዳኖስ።

፳፩ እስመ አይበሳ እግዚአብሔር ለማየ ዮርዳኖስ ቅድሜነ እስከ ነዐዱ።

፳፪ በከመ ገብራ እግዚአብሔር ለባሕረ ኤርትራ እንተ አይበሳ እግዚአብሔር አምላክነ እምቅድሜነ እስከ ኅለፍነ፣ ከመ ያእምሩ ኵሉ አሕዛበ ምድር ከመ ጽኑዕ ውእቱ ኃይሉ ለእግዚአብሔር ወከመ ትፍርህዎ አንትሙኒ ለእግዚአብሔር አምላክነ በኵሉ ግብሩ።

ምዕራፍ ፭።

፩ ወእምዝ ሶበ ሰምዑ ኵሉ ነገሥተ አሞሬዎን እለ ሀለዉ ማዕዶተ ዮርዳኖስ መንገለ ባሕር ወኵሉ ነገሥተ ፊንቂስ እለ መንገለ ባሕር ከመ አይበሳ እግዚአብሔር ለተከዜ ዮርዳኖስ እምቅድመ ገጾሙ ለደቂቀ እስራኤል ተመስወ ልቦሙ ወተጠበዩ ወኅጥኡ ዘይሔልዩ እምቅድመ ገጾሙ ለደቂቀ እስራኤል።

፪ ወእምድኅረ እማንቱ መዋዕል ይቤሎ እግዚአብሔር ለኢያሱ ግበር ለከ መጣብሐ ዘእብን እምእብነ እዝኅ ወንበር ወግዝሮሙ ለደቂቀ እስራኤል ዳግመ።

፫ ወገብረ ሎቱ ኢያሱ መጣብሐ ዘእብነ እዝኅ ወገዘሮሙ ለደቂቀ እስራኤል በውስተ መከን ዘስሙ ወግረ ቍልፈት።

፬ ወበበይነ ዝንቱ ገዘሮሙ ኢያሱ ለኵሉ ሕዝብ እለ ወፅኡ እምግብጽ ኵሉ ተባዕቶሙ ወኵሉ ሕዝብ እደው

ለሰልፍ አፋቸውን ታጥቀው የኢያሪኮን አገር ያጠፉት ዘንድ አራት መቶ ሰዎች በእግዚአብሔር ትእዛዝ ተሻገሩ። ዘኁ፡ ፴፪ ፳፯፣ ኢያ፡ ፩፡፲፬።

በያዚችም ቀን እግዚአብሔር ኢያሱን በእስራኤል ልጆች ሁሉ ፊት አከበረው፣ ከፍ ከፍ አደረገው፣ እሱ በሕይወት በኖረበት ዘመን ሁሉ ሙሴን ይፈሩት እንደነበረ ፈሩት። ኢያ፡ ፫ ፯።

እግዚአብሔር ኢያሱን እንዲህ አለው፤ ታቦትን የተሸከሙ ካህናት ከዮርዳኖስ መካከል ይወጡ ዘንድ እዘዛቸው። ዘፀ፡ ፳፫ ፲፯።

ኢያሱም ካህናቱን ከዮርዳኖስ ውጡ ብሎ አዘዛቸው። ዘፀ፡ ፳፭ ፲፯። ራእ፡ ዮሐ፡ ፲፩ ፲፱።

የእግዚአብሔር የሕጉን ማደሪያ ታቦትን የተሸከሙ ካህናት ከዮርዳኖስ መካከል በወጡ ጊዜ እግሮቻቸውም የብስን በረገጡ ጊዜ እንዲህ ሆነ የዮርዳኖስ ውኃ ፈጥኖ ወደ ቦታው ተመለሰ፣ እንደ ቀድሞውም ሄዶ እስከ ዳርቻው ደረሰ። ኢያ፡ ፫ ፯፣ ፫፡፲፭።

ሚያዝያ በበተ በዓሥረኛው ቀን ሕዝቡ ከዮርዳኖስ ወጡ፣ ከኢያሪኮም ወደ ፀሐይ መውጫ ወደ ገልገላ ተጓዙ። ፩ ሳሙ፡ ፲፩ ፲፬ - ፲፭።

ኢያሱም እነዚያን ዓሥራ ሁለቱን ደንጊያዎች በገልገላ አቆማቸው። ኢያ፡ ፭ ፱።

ኢያሱ የእስራኤል ልጆች እንዲህ አላቸው፤ ልጆቻችሁ እነዚህ ደንጊያዎች ምንድር ናቸው ብለው በጠየቋችሁ ጊዜ፣ ይህን ዮርዳኖስን እንደ ደረቅ (ምድር) ተሻግረነዋልና ስለዚህ ነው ብላችሁ ለልጆቻችሁ ንገሩዋቸው።

ፈጣሪያችን እግዚአብሔር እስክናልፍ ድረስ የኤርትራን ባሕር ከፊታችን እንዳደረቃት ይህችን ዮርዳኖስንም እስክንሻገር ድረስ ከፊታችን አደርቋታልና።

ፈጣሪያችን እግዚአብሔር እስክንሻገር ድረስ የኤርትራን ባሕር ከፊታችን እንዳደረቃት በምድር ያሉ አሕዛብ ሁሉ የእግዚአብሔር ኃይል ጽኑ እንደሆነ ያውቁ ዘንድ እናንተም ፈጣሪያችን እግዚአብሔርን በሥራው ሁሉ ትፈሩት ዘንድ ዮርዳኖስን በደረቅ ተሻግረነዋልና ስለዚህ ነው።

ምዕራፍ ፭።

ከዚህ በኋላ በባሕር አንጻር የሚኖሩ የፊንቂስ ነገሥታት ሁሉና ከዮርዳኖስ ማዶ በባሕር አንጻር የሚኖሩ የአሞሬዎን ነገሥታት ሁሉ እግዚአብሔር ከእስራኤል ልጆች ፊት የዮርዳኖስን ፈሳሽ እንዳደረቃት በሰሙ ጊዜ ልቡናቸው እንደ ሰም ቀለጠ፣ ጠፋም፣ በእስራኤልም ልጆች ፊት አስበው የሚናገሩትን አጡ። ዘፀ፡ ፲፭ ፲፬።

ከነዚያ ወራቶችም በኋላ እግዚአብሔር ኢያሱን ከቡልጭት ድንጋይ የድንጋይ ሻፎ ሥራ፣ ተቀምጠህም የእስራኤልን ልጆች ዳግመኛ ግረዛቸው አለው። ዘፀ፡ ፬ ፳፭።

ኢያሱም የድንጋይ ቡልጭት ሻፎን ሠርቶ የግርዛት ኮረብታ በሚባለው ቦታ የእስራኤልን ልጆች ገረዛቸው።

ስለዚህም ከግብጽ የወጡት ወንዶች ሁሉ ከግብጽ ከወጡ በኋላ በምድረ በዳ ጕዳና የሞቱም አርበኞች

መስተቃትላን እለ ሞቱ በገዳም በፍኖት ወሚአሙ እምግ ብጽ ከኑ ግዙራነ ።

፭ ወኵሉ ሕዝብ እለ ተወልዱ በፍኖት በገዳም ወሚአሙ እምድረ ግብጽ እስመ እሙንቱ ኢኮኑ ግዙራነ ።

፮ እስመ አርብዐ ዓመተ ሖሩ እስራኤል ውስተ ገዳም ዘመድበራ እስከ ተፈጸመ ኵሉ ሕዝብ መስተቃትላን እለ ወፅኡ እምድረ ግብጽ እለ ክሕዱ ትእዛዘ እግዚአብሔር ።

፯ ወይቤሎሙ እግዚአብሔር ከመ ኢይርአይዋ ለይእቲ ምድር ዘመሐለ እግዚአብሔር ለአበዊነ ከመ የሀበነ ምድረ እንተ ትውኅዝ ሐሊበ ወመዓረ ።

፰ ወህየንተ ዚአሆሙ አቀመ ውሉዶሙ ዘገዘሮሙ ኢያሱ እስመ ኢኮኑ ግዙራነ እስመ በፍኖት ተወልዱ ወኢተገዝሩ ።

፱ ወአመ ተገዝሩ ነበሩ ትዕይንት ወወዓሉ እስከ የሐይዉ ።

፲ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለኢያሱ ናሁ ዮም በዛቲ ዕለት አውፃእኩ ትዕይርቶሙ ለግብጽ እምኔክሙ ወሰመዩ ስሞ ለውእቱ መካን ገልገላ እስከ ዮም ወእስከ ዛቲ ዕለት ።

፲፩ ወኀደሩ ደቂቀ እስራኤል ውስተ ገልገላ ወገብሩ ፋሲካ አመ ፲ሡሩ ወረቡዑ ለሠርቀ ቀዳሚ ወርኅ በሠርክ በዐረቢሃ ለኢያሪኮ በማዕዶተ ዮርዳኖስ በውስተ ገዳም ወበልዑ እምእክለ ምድር ናእተ ሐዲሰ ።

፲፪ ወበይእቲ ዕለት ኀልቀ መና በሳኒታ እምዘበልዑ እክለ ምድር ወኢረከቡ እንከ መና ደቂቀ እስራኤል ዳግመ እስመ አረሩ ብሔረ ፊንቆን በውእቱ ዓመት ።

፲፫ ወከነ እንዘ ሀለወ ኢያሱ ውስተ ኢያሪኮ ነጸረ በአዕይንቲሁ ወርእየ ብእሴ ይቀውም ቅድሜሁ ወሰይፍ ምሉሕ ውስተ እዴሁ ወቀርበ ኢያሱ ወይቤሎ እምሰብእ ዚአነኑ አንተ አው እምፀርነ ።

፲፬ ወይቤሎ አንሰ መልአከ ኃይሉ ለእግዚአብሔር ወይእዜ በጻሕኩ ።

፲፭ ወወድቀ ኢያሱ በገጹ ወሰገደ ሎቱ ውስተ ምድር ወይቤሎ ምንት አቀመከ ኀበ ገብርከ ።

፲፮ ወይቤሎ መልአከ ኃይሉ ለእግዚአብሔር ለኢያሱ ፍታሕ አሣእኒከ እምእገሪከ እስመ መካን ኀበ ትቀውም ምድር ቅድስት ይእቲ፣ ወገብረ ኢያሱ ከማሁ ።

ምዕራፍ ፮ ።

፩ ወኢያሪኮሰ ዕፁት ይእቲ ወጥቅም ላዕሌሃ ወአልቦ ዘይወፅእ እምውስቴታ ወአልቦ ዘይበውእ ኀቤሃ ።

፪ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለኢያሱ ናሁ አገብእ ለኢያሪኮ ውስተ እደዊክሙ ወለንጉሥ ዘውስቴታ ወእለ ጽኑዓን እሙንቱ ወኀያላን ።

ሁሉ ተገርዘው ነበርና ። ዘኁ፣ ፲፬ ፳፱፣ ፳፮ ፷፬ ።
ዘዳ፣ ፩ ፫ ። ዕብ፣ ፫ ፲፩ ።

ከግብጽም ምድር ከወጡ በኋላ በምድረ በዳ ጉዳና የተወለዱት ሕዝቡ ሁሉ እነሰቸው አልተገረዙም ነበርና ስለዚህ ነው ። ዘፀ፣ ፲፬ ፳፱፣ ዘዳ፣ ፪ ፲፮ ።

ከግብጽ የወጡ የእግዚአብሔርን ትእዛዝ የካዱ አርበኞች ሰዎች ሁሉ እስኪጠፉ ድረስ መድበራ በሚባል ምድረ በዳ አርባ ዘመን ስለ ዞሩ ።

ተድላ ደስታ የሚገኝበትን አገር ይሰጠን ዘንድ እግዚአብሔር ላበቶቻችን የማለላቸውን ያችን አገር እንዳያዩዋት እግዚአብሔር ነገራቸው ። ዘፀ፣ ፫ ፰፣ ዘኁ፣ ፲፬ ፴፫ ።

በመንገድ ተወልደው አልተገረዙም ነበርና፣ ኢያሱ የገረዛቸው ልጆቻቸውን ስለነሱ ፈንታ ተካ ።
ዘፍ፣ ፴፬ ፳፭ ። ሌዋ፣ ፲፰ ፫ ። ፩ ሳሙ፣ ፲፬ ፮ ።

እነዚህም በተገረዙ ጊዜ እስኪድኑ ድረስ ሠራዊቱ ሰፈር አድርገው ዋሉ ። ዘፍ፣ ፴፬ ፳፭ ።

እግዚአብሔርም ኢያሱን እንዲህ አለው፤ እነሆ ዛሬ በዚህች ቀን የግብጻውያንን ተግዳሮት ከናንተ አራቅሁላችሁ አለው፣ ኢያሱም የዚያን ቦታ ስም ገልገላ አለው፣ እስከዛሬ እስከዚችም ቀን ገልገላ ይባላል ።

የእስራኤልም ልጆች በገልገላ አደሩ፣ መጀመርያ ወር የሚሆን ሚያዝያ በባተ በሥራ አራተኛው ቀን በኢያሪኮ ምዕራብ በዮርዳኖስ ማዶ በምድረ በዳው በሠርክ ፋሲካን (በዓል) አደረጉ፣ ከምድሪቱም የተገኘውን አዲሱን እኽል ቂጣ አድርገው በሉ ። ዘፀ፣ ፲፪ ፮፣ ኢያ፣ ፫ ፰ ።

የዚያን አገር እኽል ከበሉ በኋላ በማግሥቱ በዚያች ቀን መናው ቀረ (ቆመ)፣ በዚያው ዓመት የፊንቆንን አዝመራ ዘርፈዋልና (በልተዋልና) ዳግመኛ የእስራኤል ልጆች መና አላገኙም ። ዘፀ፣ ፲፮ ፴፭ ።

ኢያሱም በኢያሪኮ ሳለ በእጁ የተመዘዘ ሰይፍን የያዘ ሰው በፊቱ ቁሞ በዓይኖቹ አይቶ፣ ኢያሱ ቀርቦ ከኛ ሰዎች ወገን ነህን፤ ወይስ ከጠላቶቻችን ወገን ነህ፤ አለው ።
ዘኁር፣ ፩ ፰ ። ግብ፣ ሐዋ፣ ፩ ፲ ።

እኔስ እግዚአብሔር ኃይሉን የሚገልጥበት መልአክ ነኝ አሁንም ወዳንተ መጥቻለሁ አለው ።

ኢያሱም ወደ ምድር በግንባሩ ተደፍቶ ሰገደለት፣ በኔ በባሪያህ ዘንድ ምን አቁሞ ኸል፤ አለው ።

የእግዚአብሔር የሠራዊቱም አለቃ ኢያሱን የቆምክ በት ምድር የከበረች ምድር ናትና ጫማህን ከእግርህ አውልቅ አለው፣ ኢያሱም እንዳለው አደረገ ።

ምዕራፍ ፮ ።

ኢያሪኮ ግን ተዘግታ ነበር ቅጥርም ነበራት፣ ከዷ የሚ ወጣ ወደዷም የሚገባ አልነበረም ።

እግዚአብሔር ኢያሱን እንዲህ አለው፤ በውስጧ ያለውን ንጉሷን ከኃያላኑና ከአርበኞቹ ጋር በእጃችሁ እጥላታለሁ ። ዘዳ፣ ፯ ፳፬ ፣ ኢያ፣ ፪ ፳፬ ።

፫ ወአንትሰ አቅሞሙ ለዕሌሃ ውስተ ዐውዳ ለኵሎሙ መስተቃትላን ወይዑድዋ ለሀገር ኵሎሙ እደው መስተቃትላን ውስተ ዐውዳ ለይእቲ ሀገር በበምዕር ወከማሁ ግበሩ ሰዱሰ መዋዕለ ።

አንተ ግን በኢያሪኮ በዙርያዋ ኃያላኑን አቁማቸው ፡ ኃያላኑ ሰዎች ሁሉ በዚያች አገር ዙርያ አገሪቱን አንድ አንድ ጊዜ ይዙርዋት እንደዚሁም ስድስት ቀን አድርጉ። ነህ፡ ፱ ፳፬ ። ዳን፡ ፭ ፲፰ - ፲፱ ።

፬ ወሰብዓቱ ካህናት ይንሥኡ ሰብዓተ አቅርንተ ዘኢዮቤል ቅድመ ታቦት ፡ ወአመ ሳብዕት ዕለት ሰብዐ ይዑድዋ ለሀገር ወይንፍሑ ካህናት በእሙንቱ አቅርንት ።

ሰባቱም ካህናት በታቦት ፊት በኢዮቤል የሚነፋ ሰባት ቀንደ መለከት ይያዙ ፡ በሰባተኛይቱ ቀን ግን አገሪቱን ሰባት ጊዜ ይዙርዋት ካህናቱም ቀንደ መለከቱን ይንፉ።

፭ ወሶበ ነፍሑ በእሙንቱ አቅርንት ዘኢዮቤል እምከመ ሰማዕክሙ ቃለ ቀርን ለይወውዑ ኵሎሙ አሕዛብ ኅቡረ ፡ ወእምከመ ወውዑ አሙንቱ ይወድቅ ለሊሁ አረፋቲሃ ለሀገር ታሕቲሆሙ ወይበእ እንከ ኵሉ ሕዝብ ወይሩጽ አሐዱ አሐዱ ቅድመ ገጹ ውስተ ሀገር ።

በአርበ ዘጠኝ ዘመን የሚነፉ እነዚያን ቀንደ መለከት በነፉ ጊዜ የቀንደ መለከቱን ድምፅ ከሰማችሁ በኋላ ሕዝቡ ሁሉ አንድነት ይደንፉ ፡ እነዚያም ከደነፉ በኋላ የአገሪቱ ቅጽር በበታቻቸው ይወድቃል ፡ ከዚህ በኋላ ሕዝቡ ሁሉ ይግባ ፡ አንዱም አንዱም በፊቱ ወደ አገሪቱ ይሩጥ አለው ። ዘፀ፡ ፲፱ ፲፫ ፡ መሰ፡ ፳ ፴፯ ።

፮ ወፀውዖሙ ኢያሱ ለካህናት ወይቤሎሙ ንሥኡ ታቦተ ሕግ ወሰብዐቱ ካህናት ይንሥኡ ሰብዓተ መጣቅዕተ ዘኢዮቤል በቅድመ እግዚአብሔር ።

ኢያሱም ካህናቱን ጠርቶ የሕጉ ማደሪያ ታቦትን ይያዙ ሰባቱም ካህናት በአርበ ዘጠኝ ዘመን የሚነፉ ሰባቱን ቀንደ መለከት በእግዚአብሔር ፊት ይያዙ አላቸው ።

፯ ወይቤሎሙ አዝዝዎሙ ለሕዝብ ከመ ይሑሩ ወይዑድዋ ለሀገር ወመስተቃትላንኒ ይሑሩ ምስለ ንዋየ ሐቅሎሙ ቅድመ ታቦተ ሕጉ ለእግዚአብሔር ።

ሕዝቡም ሂደው አገሪቱን ይክቧት ዘንድ አዘዟቸው አርበኞቹም ከሚዳ ጸብታቸው ጋራ በእግዚአብሔር ሕግ ማደሪያ ታቦት ፊት ይሄዱ ዘንድ አዘዙዋቸው አላቸው ።

፰ ወነሥኡ ሰብዐቱ ካህናት ሰብዓተ መጣቅዕተ ቅዱሳነ በከመ ይቤሎሙ ኢያሱ ከመ ይሑሩ ቅድመ እግዚአብሔር ወሐዊሮሙ ይጥቅዑ በኃይል ወበትእምርት ወታቦተ ሕጉሂ ለእግዚአብሔር ትተልዎሙ ።

ኢያሱም በእግዚአብሔር ፊት ይሄዱ ዘንድ እንደ ነገራቸው ሰባቱ ካህናት ልዩ የሆኑ ሰባቱን ቀንደ መለከት ይዘው ሄዱ ፡ በሄዱም ጊዜ አሰምተው ምልክት አድርገው ይምቱ ፤ የእግዚአብሔር የሕጉ ማደሪያ ታቦትም ትከተላቸዋለች ። ኢያ፡ ፬ ፲፫ ።

፱ ወመስተቃትላንሰ ፍጽመ የሐውሩ ወካህናትኒ ይጠቅዑ በመጣቅዕት ወእለሂ ይትኬወሉ ድኅረ ታቦተ ሕጉ ለእግዚአብሔር የሐውሩ እንዘ ይነፍሑ ቀርነ ።

አርበኞች ግን በፊት ይሄዱ ነበር ፡ ካህናቱም ነጋሪቱን ይመቱ ነበር ፡ ከእግዚአብሔር ከሕጉ ማደሪያ ከታቦት በኋላ የነበሩትም ቀንደ መለከት እየመቱ ይሄዱ ነበር።

፲ ወአዘዞሙ ኢየሱ ለሕዝብ ከመ ኢይውክቱ ወአልበ ዘይሰምዕ ቃሎሙ መኑሂ ከመ ኢይፃእ ቃል እምአፉሆሙ እስከ አመ ውእቱ ይኤዝዞሙ ከመ ይወውዑ ።

ኢያሱም ሕዝቡ ግርግር እንዳይሉ አዘዛቸው ፡ ከፋቸውም ቃል እንዳይወጣ ይደነፉም ዘንድ እሱ እስኪያዛቸው ድረስ ማንም ማን ቃላቸውን የሚሰማ እንዳይኖር አዘዛቸው ።

፲፩ ወሖረት ታቦተ ሕጉ ለእግዚአብሔር ወዖደታ ለሀገር ወእምዝ ገብአት ውስተ ትዕይንት ወቤተት ህየ ።

የእግዚአብሔር የሕጉ ማደሪያ ታቦትም ሂዳ አገሪቱን ዞረቻት ፡ ከዚህ በኋላ ወደ ሰፈር ተመልሳ በዚያ አደረች።

፲፪ ወበሳኒታ ዕለት ተንሥአ ኢያሱ በጽባሕ ወካህናትኒ ፆሩ ታቦተ ሕጉ ለእግዚአብሔር ።

በማግሥቱም ሲነጋ ኢያሱ ተነሣ ፡ ካህናቱም የእግዚአብሔር የሕጉ ማደሪያ ታቦትን ተሸከሙ ።

፲፫ ወሰብዐቱ ካህናት ነሥኡ ሰብዓተ መጣቅዕተ ቅዱሳነ ወሖሩ ቅድመ ታቦተ ሕጉ ለእግዚአብሔር ወይተልዉ መስተቃትላን ወእምዝ ይተልዉ እለ ተርፉ ሕዝብ ወየሐውሩ ድኅረ ታቦተ ሕጉ ለእግዚአብሔር እንዘ ይነፍኁ በአቅርንት ወካህናትኒ ይጠቅዑ በመጣቅዕት ።

ሰባቱም ካህናት ልዩ የሆኑ ሰባቱ ቀንደ መለከት ይዘው በእግዚአብሔር በሕጉ ማደሪያ ታቦት ፊት ይሄዱ ነበር አርበኞቹም ይከተሉ ነበር ፡ ከዚህ በኋላ የቀሩት ወገኖች ቀንደ መለከቱን እየነፉ በእግዚአብሔር በሕጉ ማደሪያ ታቦት በኋላ ይሄዱ ነበር ፡ ካህናቱም ቀንደ መለከቱን ይመቱ ነበር ። ፩ ዜና መዋ፡ ፲፭ ፳፬ ።

፲፬ ወኵሉ ሕዝብ ዘተርፉ ዖድዋ ለሀገር አሐደ ጊዜ አመ ሳኒታ ዕለት እንዘ ይቀርብዋ ወእምዝ ካዕበ ገብኡ ውስተ ትዕይንት ወከመዝ ገብሩ ሰዱሰ መዋዕለ ።

የቀሩት ሕዝቡ ሁሉ በማግሥቱ ቀርበው አገሪቱን አንድ ጊዜ ዞሯት ከዚህ በኋላ ዳግመኛ ወደ ሰፈር ተመለሱ ስድስትም ቀን እንዲህ አደረጉ ።

፲፭ ወኮነ አመ ሳብዕት ዕለት ተንሥኡ ጊዜ ይገውሕ ጽባሕ ወዖድዋ ከማሁ ለሀገር ሰብዓ ወዳእሙ በይእቲ ዕለት ዖድዋ ሰብዓ ለሀገር ።

በሰባተኛውም ቀን እንዲህ ሆነ ፡ ጎሕ በቀደደ ጊዜ አገሪቱን እንደዚሁ ሰባት ጊዜ ዞሯት ፡ በዚያች ቀን ብቻ አገሪቱን ሰባት ጊዜ ዞሯት ።

፲፮ ወኮነ ሶበ ዖድዋ ሰብዐ ለሀገር ጠቅዑ ካህናት በመጣ

አገሪቱን ሰባት ጊዜ በዞሯት ጊዜ እንዲህ ሆነ ፡ ካህናቱ

ቅዕቲሆሙ ወይቤሎሙ ኢያሱ ለደቂቀ እስራኤል ወውዑ
እስመ አግብአ እግዚአብሔር ለነ ።
፲፯ ወአሕረምናሃ ለዛቲ ሀገር ወኵሉ ዘውስቴታ ይኩን
ለእግዚአብሔር ጸባኦት ዘእንበለ ራዓብ ዘማ እንተ ታሐ
ይዉ ኪያሃ ወኵሎ ዘሀለወ ውስተ ቤታ እስመ ኀብአቶሙ
ለሰብአ ዐይን እለ ፈነውነ ።
፲፰ ወአንትሙ ዐሕቱ ዑቁ ኢትንሥኡ እምዘሐሩም ዘአሕ
ረምነ ወኢትፍትዉ ወኢትንሥኡ እምኔሁ ወከመ እኩይ
ትገብርዋ ርግምተ ለትዕይንት ወትቀጠቅጡነ ።
፲፱ ወኵሉ ወርቅ ወብሩር ወብርት ወሐጺን ቅዱስ ይኩን
ለእግዚአብሔር ወውስተ መዝገቡ ይባእ ።
፳ ወወውዑ ሕዝብ ወካህናትኒ ጠቅዑ በመጣቅዕቲሆሙ
ወኀቡረ ወውዑ ሕዝብ በዐቢይ ውውዓ ወጽንዐ ወወድቀ
ኵሉ ዓረፋቲሃ ዘዐውዳ ወቦኡ ኵሉ ሕዝብ ውስተ ሀገር
ወኵሎሙ ሮጹ ውስተ ሀገር ቅድሜሆሙ ወረከብዋ ለሀገር ፤
፳፩ ወአሕረማ ኢያሱ ወኵሎ ዘሀለወ ውስቴታ ለይእቲ
ሀገር እምተባዕት እስከ አንስት እምንኡሶሙ እስከ ልሂ
ቆሙ ወእስከ ላሕም ወበግዕ ወእስከ አድግ ቀተሉ በሐፂን።
፳፪ ወይቤሎሙ ኢያሱ ለእልክቱ ክልኤቱ ወራዙት ሰብአ
ዐይን እለ ርእይዋ ለብሔር ሑሩ ውስተ ቤታ ለእንታክቲ
ብእሲት ዘማ ወአውፅእዋ እምህየ ወኵሎ ዘሀለወ ምስሌሃ
በከመ መሐልክሙ ላቲ ።
፳፫ ወቦኡ እልክቱ ክልኤቱ ወራዙት ሰብአ ዐይን እለ
ርእይዋ ለይእቲ ሀገር ውስተ ቤተ ራዓብ ዘማ ወአውፅእዋ
ወለአቡሃ ወለእማ ወለአኀዊሃ ወለኵሉ ዘመዳ ወኵሎ ዘባቲ
ወአብጽሕዋ እስከ አፍአ ውስተ ትዕይንቶሙ ለእስራኤል ፡
፳፬ ወውዕየት ሀገር ምስለ ኵሉ ዘውስቴታ በእሳት ዘእን
በለ ወርቅ ወብሩር ወኵሉ ብርት ወሐፂን ዘአብኡ ውስተ
ዘአብኡ መዛግብተ ቤተ እግዚአብሔር።
፳፭ ወራዓብ ዘማ ወኵሉ ቤተ አቡሃ ዘአሕየወ ኢያሱ ነበ
ረት ውስተ እስራኤል እስከ ዛቲ ዕለት እስመ ኀብአቶሙ
ለሰብአ ዐይን እለ ፈነወ ኢያሱ ከመ ይርአይዋ ለሀገረ
ኢያሪኮ ።
፳፮ ወአምሐለ ኢያሱ በይእቲ ዕለት ወይቤ ርጉም ለይ
ኩን ዘያነሥኣ ለዛቲ ሀገር ፤ በበኵሩ ለይሣርራ ፤ ወበደኃሪ
ወልዱ ለያቅም ኖኃተ አንቀጺ ።
፳፯ ወሀለወ እግዚአብሔር ምስለ ኢያሱ ወበጽሐ ስሙ
ውስተ ኵሉ ምድር ።

ምዕራፍ ፯ ።

፩ ወአበሱ ደቂቀ እስራኤል ዐቢየ አበሳ ወነሥአ አካን
ወልደ ከርሚ ወልደ ዘንበሪ ወልደ ዛራ ዘእምነገደ ይሁዳ
እምዘአሕረሙ ወተምዐ እግዚአብሔር ላዕለ ደቂቀ እስራ
ኤል ።
፪ ወፈነወ ኢያሱ እደወ ውስተ ጋይ እምኢያሪኮ እንተ
መንገለ አዊን መንገለ ጽባሒሃ ለቤቴል ወይቤሎሙ ዕርጉ
ወረአይዋ ለጋይ ወዐርጉ እሙንቱ እደው ወርአይዋ ለጋይ ።

ነጋሪታቸውን መቱ፤ ኢያሱም እግዚአብሔር በእጃችን
ጥሎልናልና የእስራኤልን ልጆች ድንፉ አላቸው ።
ይህችንም አገር አጥፍተናታልና እነዚያን የላክናቸ
ውን ጐብኝዎች ሠውራቸዋለችና በቤቷ ካለው ሰው ሁሉ
ና እሷን ከምታድኑዋት ከራዓብ ዘማ በቀር በውስጧ ያለ
ው ገንዘብ ሁሉ ለአሸናፊው ለእግዚአብሔር ይሁን ።
እናንተ ግን እርም ብለን ከተነውነው ገንዘብ አንዳች
ወስዱ ዕወቁ፤ ከዚህ ወዳችሁ አትውሰዱ፤ ብትወስዱ
ግን ይህችን ወገን የተረገመች ታደርጓታላችሁ እኛንም
ታጠፉናላችሁ ። ዘፍ፡ ፴፬ ፴፤ ኢያ፡ ፯ ፳፭ ።
ወርቁና ብሩ፤ ብረቱና ናሱ ሁሉ ለእግዚአብሔር የተ
ለየ ይሁን ወደ ዕቃ ቤቱም ይግባ ።
ሕዝቡም ደነፉ፤ ካህናቱም ነጋሪታቸውን መቱ፤ ወገ
ኖችም በብዙ በጽኑ ድንፋታ ደነፉ፤ በዙርያዋ ያለ ቅጥሯ
ሁሉ ፈረሰ፤ ሕዝቡም ሁሉ ወደ አገር ገቡ፤ ሁሉም ወደ
ፊታቸው ሮጡ፤ አገሪቱንም እጅ አደረጓት ።
ኢያሱም አጠፋት ፤ በዚያች አገር ያለውንም ሁሉ
ከወንዱ እስከ ሴቱ፤ ከታናሹ እስከ ሽማግሌው፤ ከላሙ
እስከ በጉ፤ እስከ አህያውም ድረስ በጦር አጠፋ ።
ኢያሱ አገሪቱን ያዩዋት እሊያን ሁለቱ ጐልማሶች
ጐብኝዎች ወደዚያች ዘማ ሴት ሂዱችሁ ከዚያ አውጧት
እንደ ማላችሁላት ከርሷ ጋር ያለውን ሁሉ አውጡ
አላቸው ። ኢያ፡ ፪ ፲፬፤ ዕብ፡ ፲፩ ፴፩ ።
ያችን አገር ያዩዋት እነዚህ ሁለቱ ጐልማሶችም ወደ
ራዓብ ዘማ ገብተው አወጧት፤ እናትና አባቷን ዘመዷን
ሁሉና ወንድሞቿን ያላትን ሁሉ አወጧቸው ወደ እስራ
ኤልም ሰፈር አደረሷት ። ኢያ፡ ፪ ፲፫ ።
ወደ ቤተ እግዚአብሔር ዕቃ ቤት ከገቡት ከወርቁና
ከብሩ ከብረቱና ከናሱ ሁሉ በቀር አገሪቱ በእሳት ተቃ
ጠለች ። ኢያ፡ ፯ ፲፱፤ ማቴ፡ ፩ ፭ ።
ራዓብ ዘማ ኢያሱ ከዳናቸው ከአባቷ ወገኖች ሁሉ
ጋር የኢያሪኮን አገር ያዩዋት ዘንድ ኢያሱ የላካቸውን
ጐብኝዎች ሠውራቻቸዋለችና እስከዚች ቀን ድረስ ከእስራ
ኤል ልጆች ጋራ ኖረች ።
ኢያሱ በዚያች ቀን ይህችን አገር አቀናለሁ የሚል
ሰው የተረገመ ይሁን፤ መሠረቷን ሲጀምር የበኩር ልጁ
ይሙት፤ የደጇም በሯንም ሲያቆም ታናሽ ልጁ ይጥፋ
ብሎ አማለ ። ዘኍ፡ ፩ ፳፩ ። ፩ ነገ፡ ፲፮ ፴፬ ።
እግዚአብሔር ከኢያሱ ጋራ በረድኤት ኖረ፤ ስሙም
በራቱ መዓዝነ ዓለም ደረሰ (ታወቀ) ። ኢያ፡ ፩ ፭፤ ፱ ፱ ።

ምዕራፍ ፯ ።

የእስራኤል ልጆች ብርቱ በደልን በደሉ፤ ከነገደ ይሁ
ዳ የተወለደ የዛራ ልጅ የሚሆን የዘንበሪ ልጅ የከርሚ
ልጅ አካን፤ እርም ከሉት ገንዘብ ወሰደ፤ እግዚአብሔርም
በእስራኤል ልጆች ላይ ተቈጣ (ፈረደ) ። ኢያ፡ ፯ ፳፭ ።
ኢያሱ የቤቴል ምሥራቅ ከምትሆን በአዊን አጠገብ
ካለች ከኢያሪኮ ወደ ጋይን እዩዋት ብሎ ሰዎችን
ላከ፤ እነዚያም ሰዎች ወጥተው ጋይን አዩዋት ።

፫ ወገብኡ ኀበ ኢያሱ ወይቤልዎ ኢይዕርግ ኵሉ ሕዝብ አላ ዕሥራ ምእት አው ሠላሳ ምእት አደው ይዕርጉ ወይትቃተልዋ ለይእቲ ሀገር ወኵሎሰ ሕዝበ እግዚአብሔር ኢትሰድ ህየ እስመ ውኁዳን እሙንቱ ።

ወደ ኢያሱም ተመልሰው ሁለት ሺሕ ወይም ሦስት ሺሕ ሰዎች ወጥተው ጋይን አገር ይምቷት እንጂ ሕዝቡ ሁሉ አይውጡ ጥቂቶች ናቸውና የእግዚአብሔርን ወገኖች ግን ወደዚያ አትውሰድ አሉት ። ዘሌ፡ ፳፯ ፲፯ ።

፬ ወዐርጉ እምሕዝብ ዘየአክሉ ሠላሳ ምእት ወአንትዕዎሙ ሰብአ ጋይ ወጐዩ እምቅድመ ገጾሙ ።

ከሕዝቡም ሦስት ሺሕ ሰዎች ያህል ወጡ፤ በጋይ ያሉትም ሰዎች አበረሩዋቸው፤ ከፊታቸውም ሸሹ ።

፭ ወቀተሉ እምኔሆሙ በውስተ ጋይ ሠላሳ ወስድስተ እደወ፤ ወእምዝ ዴገንዎሙ እምኀበ አንቀጽ እስከ አጥፍእዎሙ ወቀተልዎሙ በውስተ ሙራድ ወደንገፀ ልበሙ ለሕዝብ፤ ወኮነ ከመ ማይ ።

ከነሱም በጋይ ሠላሳ ስድስት ሰዎች ገደሉ፤ ከዚህ በኋላ እስኪያጠፉዋቸው ድረስ ደርሰው ከአደባባዩ ጀምረው ተከተሏቸው፤ በቍልቍለቱም ገደሏቸው፤ የሕዝቡም ልቡና ደነገጠ፤ እንደ ውኃም ቀዘቀዘ። ኢያ፡ ፲ ፲፩ ።

፮ ወሠጠጠ አልባሲሁ ኢያሱ ወወድቀ በገጹ ውስተ ምድር ቅድመ ታቦቱ ለእግዚአብሔር እስከ ሠርክ ውእቱ ወሊቃናቲሆሙ ለእስራኤል ወወደዩ መሬተ ውስተ ርእሶሙ ።

ኢያሱም ልብሱን ቀደደ፤ በእግዚአብሔርም ማደሪያ በታቦት ፊት እስከ ሠርክ ድረስ እሱ ከእስራኤል አለቆች ጋራ በግንባሩ ወደ ምድር ወደቀ፤ በራሳቸውም ላይ ትቢያን ነሰነሱ ፡ ፩ ሳሙ፤ ፬ ፲፪፣ ፪ ሳሙ፤ ፩ ፲፩ ።

፯ ወይቤ ኢያሱ ገነይኩ ለከ እግዚኦ እግዚኦ፤ ለምንት አዕደውኮ አዕደዎሙ ገብርከ ለእሉ ሕዝብ እምዮርዳኖስ ከመ ታግብኦሙ ውስተ እደዊሆሙ ለአሞሬዎን ወከመ ያጥፍኡነ ሶበ ኀደርነ ወነበርነ ማዕዶተ ዮርዳኖስ እግዚኦ ።

ኢያሱ አቤቱ! አቤቱ! ተገዛሁልህ በአሞሬዎን እጅ ትጥላቸው ዘንድ ያጠፉንም ዘንድ እኒ አገልጋይህ እነዚህን ሰዎች ከዮርዳኖስ ለምን አሻገርኋቸው፤ እነዚህ ከሚያጠፉን በዮርዳኖስ ማዶ ብንኖር በተሻለን ነበር አለው።

፰ ወምንተ እንከ እብል ናሁ ሚጠ እስራኤል ዘበኖ ኀበ ፀሩ ።

እነሆ እስራኤል ጀርባውን ወደ ጠላቱ መለሰ እንግዲህ ወዲህ ምን እላለሁ፤ አለ ። ዘፀ፡ ፴፫ ፴፪ ።

፱ ወእምከመ ሰምዑ ከነዓን ወኵሎሙ እለ ይነብሩ ውስተ ዛቲ ምድር፤ የዐግቱነ ወያጠፍኡነ እምድር፤ ወምንተ ትሬሲ ለስምከ ዐቢይ ።

በዚች አገር የሚኖሩ ሰዎች ሁሉና የከነዓን ሰዎች ጥፋታቸውን ከሰሙ ከበው ከአገር ያጠፉናል ለታላቁ ስምህስ ምን ታደርጋለህ፤ አለ ። ዘፀ፡ ፴፪ ፲፪ ።

፲ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለኢያሱ ተንሥእ ወለምንት ትወድቅ አንተ በገጽከ ።

እግዚአብሔርም ኢያሱን ተነሥ፤ ለምን በግንባርህ ትወድቃለህ፤ አለው ። ኢያ፡ ፯ ፯ ።

፲፩ አበሱ ሕዝብ ወክሕዱ ኪዳንየ ዘተከየድኩ ምስሌሆሙ ወነሥኡ እምዘሕሩም፤ ወሰረቁ ወወደዩ ውስተ ንዋያቲሆሙ ።

ሕዝቡ በደሉ ከነሱ ጋር የተማማልኩት መሐላዬን አፍርሰው እርም ከሉት ገንዘብ ወሰዱ፤ ሰርቀውም ከገንዘባቸው ጋር ጨመሩ ። ዘዳ፡ ፲፮ ፪ ።

፲፪ ወኢይክሉ እንከ ደቂቀ እስራኤል ቀዊመ ቅድመ ፀሮሙ ወይመይጡ ዘባናቲሆሙ ቅድመ ፀሮሙ እስመ ርጉማነ ኮኑ፤ ወኢይደግም እንከ ሀልዎ ምስሌክሙ ለእመ ኢያውፃእክሙ እምኔክሙ ዘርጉም ።

እንግዲህ ወዲህ የእስራኤል ልጆች በጠላቶቻቸው ፊት ቆመው መዋጋት አይችሉም የተረገሙ ሆነዋልና፤ ጀርባቸውን መልሰው ይሸሻሉ፤ አሁንም የተረገመውን ሰው ከናንተ ለይታችሁ ካላወጣችሁ እንግዲህ ወዲህ ከናንተ ጋር በረድኤት አልኖርም ። ዘኍ፡ ፲፬ ፵፭ ።

፲፫ ተንሥእ ወቀድሶሙ ወበሎሙ አንጽሑ ርእሰክሙ ለጌሠም፤ እስመ ከመዝ ይቤ እግዚአብሔር አምላከ እስራኤል ዘሕሩም ሀለወ ውስቴትክሙ ወኢትክሉ እንከ ቀዊመ ቅድመ ፀርክሙ እስከ ታሴስሉ እምኔክሙ ዘሕሩም ።

ከወደቅህበት ተነሥተህ ለያቸው፤ በውስጣቸውም የተረገመ ሰው አለና፤ የእስራኤል ፈጣሪ እግዚአብሔር ራሳችሁን ለነገ አንጹ አለ በላቸው፤ የተረገመውን ከናንተ ለይታችሁ ካላስወገዳችሁ እንግዲህ ወዲህ በጠላቶቻችሁ ቁሞ መዋጋት አትችሉም አለ በላቸው ።

፲፬ ወይጌሥ በጽባሕ ወይትጋብኡ ኵሎሙ በበሕዘቢሆሙ ወሕዝብ ዘአርአየ እግዚአብሔር ላዕሌሁ ለይትፋለጡ በበነገዶሙ ወይቁሙ፤ ወነገድ ዘአርአየ እግዚአብሔር ላዕሌሁ ለይትፋለጡ ወይቁሙ በበቤቶሙ፤ ወቤት ዘአርአየ እግዚአብሔር ላዕሌሁ ለይትፋለጡ ወይቁሙ በበብእሲሁ ።

ሲነጋ ሂደው ሁሉም በየወገናቸው ይሰብሰቡ እግዚአብሔር በላያቸው ላይ ምልክት ያሳየበቸው ወገኖች ተለይተው በየነገዳቸው ይቁሙ፤ እግዚአብሔር በላያቸው ላይ ምልክት ያሳየበቸው ወገኖች አንዱም አንዱም ሰው ተለይተው ይቁሙ ። ፩ ሳሙ፤ ፩ ፲፣ ፲፱ ፳፩ ።

፲፭ ወብእሲ ዘአርአየ እግዚአብሔር ላዕሌሁ ለያውዕዩ በእሳት ሎቱ ወለኵሉ ዘዚአሁ እስመ ክሕደ ኪዳኖ ለእግዚአብሔር ወገብረ ኀጢአተ ላዕለ እስራኤል ።

እግዚአብሔር በላዩ ላይ ምልክት ያሳየበትን ሰው የእግዚአብሔርን ሕግ አፍርሷልና፤ በእስራኤልም ላይ ኃጢአት ሠርቷልና እሱን ከወገኖቹ ጋር በእሳት ያቃጥሉት አለው ። ኢያ፡ ፯ ፲፩፣ ፩ ሳሙ፤ ፲፬ ፴፰ ።

፲፮ ወጌሠ ኢያሱ ወአስተጋብኦሙ ለሕዝብ በበሕዘቢሆሙ ወአስተርአየ ላዕለ ሕዝበ ይሁዳ ።

ኢያሱም ገሥግሦ ሕዝቡን በየወገናቸው ሰበሰባቸው በይሁዳም ወገኖች ላይ ምልክት ታየ ።

፲፯ ወተፈልጡ ሕዝበ ይሁዳ በበነገዶሙ ወአስተርአየ ላዕለ ነገደ ዛራ በቤቱ ወአስተርአየ ላዕለ ቤተ ዘንበሪ ።

የይሁዳም ወገኖች በየወገናቸው ተለዩ ፣ በዛራም ወገን ላይ ምልክት ታየ ፣ የዛራም ወገን በየወገኑ ተለየ ፣ በዘንበሪ ወገን ላይ ምልክት ታየ ። ዘኁ፡ ፳፮ ፳ ።

፲፰ ወተፈልጠ ቤተ ዘንበሪ በበብእሲሁ ወአስተርአየ ላዕለ አካን ወልደ ክርሚ ወልደ ዘንበሪ ወልደ ዛራ ዘእምሕዝበ ይሁዳ ።

የዘንበሪም ወገን አንዱም አንዱም ሰው ተለየ ፣ ከነገደ ይሁዳ የተለየ የዛራ ልጅ የዘንበሪ ልጅ በሚሆን በከርሚ ልጅ በአካን ላይ ምልክት ታየ ። ኢያ፡ ፯ ፩ ።

፲፱ ወይቤሎ ኢያሱ ለአካን ወልድየ አእኵቶ ለእግዚአብሔር አምላከ እስራኤል ወአመኖ ወአይድዐኒ ምንተ ገበርከ ወኢትኅባእ እምኔየ ።

ኢያሱም አካንን ልጄ የእስራኤል ፈጣሪ እግዚአብሔርን አመስግነው እመንውም ምን አድርገኸል ፤ አትሸሽገኝ ንገረኝ አለው ። ፩ ሳሙ፡ ፮ ፭ ፣ ኢሳ፡ ፵፪ ፲፪ ።

፳ ወአውሥአ አካን ለኢያሱ ወይቤሎ አማን አነ አበስኩ ቅድመ እግዚአብሔር አምላከ እስራኤል ፣ ከመዝ ወከመዝ ገበርኩ ።

አካንም ለኢያሱ እንዲህ ብሎ መለሰለት በእስራኤል ፈጣሪ በእግዚአብሔር ፊት እውነት በድያለሁ ፣ እንዲህና እንዲህም አድርጌአለሁ ።

፳፩ ሶበ ርኢኩ በውስተ በርበር ልብሰ ዐሥቅ አሐደ ወክልኤተ ምእተ ጠፋልሐ ብሩር ወልሳን አሐቲ እንተ ወርቅ ትአክል ሐምሳ ዲድርክመ ወተውላጣ ፈተውኩ ወነሣእኩ ወናሁ ሀለወ ድፉነ ውስተ ደብተራየ ወጠፋልሐ ብሩርኒ ሀለወ መትሕቴሁ ።

በዘረፉ መከከል አራት ኅብር አምስተኛ ወርቀ ዘቦ ፣ ሁለት መቶ ምዝምዝ ብር ፣ አምሳ ወቄት የምትሆን አንዲት ልሳነ ወርቅ በየሁ ጊዜ ለውጤን መስጠት ወድጄ ወስጃለሁ ፣ እነሆም በድንኳኔ ውስጥ ተቀብሯል ፣ ምዝምዙም ብር በበታቹ አለ ። ዘፀ፡ ፳ ፲፯ ፣ ምሳ፡ ፲፭ ፳፯ ።

፳፪ ወፈነወ ኢያሱ ደቀ ወሮጹ ኀበ ትዕይንት ውስተ ደብተራሁ ወሀለወ ዝኩ ድፉን ውስተ ደብተራሁ ወብሩርኒ ሀለወ ምስሌሁ መትሕቶ ።

ኢያሱም አሽከሮቹን ላከ ከሰፈርም ወደ ድንኳኑ ፈጥነው ሄዱ ፣ እሱም በድንኳኑ ውስጥ ተቀብሮ ብሩም በታች ሆኖ አገኘው ። ፩ ነገ፡ ፳፩ ።

፳፫ ወአውፅእዎ እምውስተ ደብተራሁ ወወሰዱ ኀበ ኢያሱ ወኀበ ኵሉ ሊቃናተ እስራኤል ወአንበሩ ቅድመ እግዚአብሔር ።

ከድንኳኑም አውጥተው ወደ እስራኤል ሁሉና ወደ ኢያሱ ወስደው በእግዚአብሔር ፊት አኖሩት ።
እንባ፡ ፪ ፱ ። ሉቃ፡ ፲፪ ፲፭ ።

፳፬ ወነሥአ ኢያሱ ለአካን ወልደ ዛራ ወለውእቱ ብሩር ወለውእቱ ልብሰ ወለይእቲ ልሳን እንተ ወርቅ ወወሰዶሙ ውስተ ቈላተ አኮር ለአካን ወደቂቁ ወለአዋልዲሁ ወለእልሕምቲሁ ወለአብግዒሁ ወለአእዱጊሁ ወለደብተራሁ ወለኵሉ ንዋዩ ወወሰዶሙ ውስተ ኤሜቃኮር ።

ኢያሱን የዛራን ልጅ አካንን ያዘው ያንን ልብስና ያንንም ብር ያችንም ልሳነ ወርቅ ይዞ አካንና ልጆቹን ላሞቹንና ሴቶች ልጆቹን አህዮቹንና በጎቹን ገንዘቡ ሁሉና ድንኳኑን ወስዶ በኤሜቃኮር ጣላቸው ። ፩ ሳሙ፡ ፲፰ ፲፯ ። ሰቆ፡ ኤር፡ ፫ ፶፫ ።

፳፭ ወይቤሎ ኢያሱ ለአካን ለምንት ሠሮከነ ለይሥሩከ እግዚአብሔር በከመ ዮም ፣ ወወገርዎ በእብን ኵሎሙ እስራኤል ወአውዐይዎሙ በእሳት ወወገርዎሙ በእብን ።

ኢያሱ አካንን ለምን አጠፋኸን እኛን ዛሬ እንዳጠፋኸን እግዚአብሔር ያጥፋህ አለው ፣ እስራኤልም ሁሉ በድንጋይ ወግረው ገደሉት ፣ በድንጋይ ወግረው በእሳት አቃጠሏቸው ።

፳፮ ወአቀሙ ሎቱ ሐውልተ እንተ እብን እስከ ዛቲ ዕለት ወአኅደገ እግዚአብሔር መንሱተ መዐቱ ወበበይነ ዝንቱ ሰመዮ ኤሜቃኮር እስከ ዛቲ ዕለት ።

እስከዚህችም ቀን ድረስ የደንጊያ ሐውልት አቆሙበት ፣ እግዚአብሔርም ፈርዶ ያመጣውን መቅሠፍት ተወ ስለዚህም እስከዚች ቀን ድረስ ኤሜቃኮር (የአኮር ሸለቆ) ብሎ ጠራው ። ኢያ፡ ፰ ፳፱ ፣ ፲ ፳፯ ።

## ምዕራፍ ፰ ።

፩ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለኢያሱ ኢትፍራህ ወኢትደንግፅ ንሥአሙ ምስሌከ ለኵሎሙ እደው መስተቃትላን ወተንሥእ ወዕርግ ውስተ ጋይ እስመ ናሁ አግባእክዎ ውስተ እዴከ ለንጉሠ ጋይ ወለሕዝቡሂ ወለሀገሩሂ ወለምድሩሂ ።

እግዚአብሔር ኢያሱን አትፍራ ፣ አትደንግጥ እነሆ የጋይን ንጉሥ ከሠራዊቱ ፣ ከአገሩ ከምድሩ ጋር በእጅህ ጥየዋለሁና አርበኞችን ጕልማሶችን ሁሉ ይዘኻቸው ተነሥተህ ወደ ጋይ ውጣ አለው ። ዘዳ፡ ፴፩ ፰ ። ኢያ፡ ፪ ፳፬ ፯ ፪ ። መዝ፡ ፵፬ ፫ ።

፪ ወትገብራ ለጋይ ወለንጉሣ በከመ ገበርከሃ ለኢያሪኮ ወለንጉሣ ወበርበረ እንስሳ በርብሩ ለርእስክሙ ወበሕቱ ፈኑ ይዕግትዋ ለሀገር እንተ መንገለ ከዋላሃ ።

ኢያሪኮን እንዳጠፋኸት ጋይን ንጉሷንም እንዳጠፋህ ንጉሷን ታጠፋለህ ፣ የከብቱንም ምርኮ ለራሳችሁ ዝረፉ ፣ ነገር ግን አገሪቱን በኋላዋ ይከቧት ዘንድ ሰው ላክ አለው ።

፫ ወተንሥአ ኢያሱ ወኵሉ ሕዝብ መስተቃትላን ወዐርጉ ውስተ ጋይ ወኀረየ ኢያሱ ሠላሰ እልፈ እደወ ጽኑዓነ ወመስተቃትላነ ወኃያላነ ወፈነዎሙ በሌሊት ።

ኢያሱም ከአርበኞች ወገኖቹ ሁሉ ጋር ተነሣ ፣ ወደ ጋይም ወጡ ፣ የጸኑ አርበኞች ኃያላን የሚሆኑ ሦስት እልፍ ሰዎችን መርጦ በሌሊት ላካቸው ።

፬ ወአዘዞሙ ወይቤሎሙ ሑሩ ከመ ታእምሩ ዕግትዋ ለሀገር እንተ መንገለ ከዋላሃ ወኢትርኅቁ በሕቁ እምሀገር ወንበሩ ኵልክሙ ድልዋኒክሙ ።

፭ ወአንሰ ወኵሉ ሕዝብ ዘምስሌየ ንቀርብ ኀበ ሀገር ወሰበ ወፅኡ ሰብአ ጋይ ወተቀበሉነ ከመ ቀዲሙ ንጐይይ እምቅድመ ገጾሙ ።

፮ ወሰበ ወፅኡ ወዴገኑነ ናርኅቆሙ እምሀገር ወይብሉ ንትዐ እሉሂ እምቅድመ ገጽነ ከመ ቀዲሙ ወንሕነሂ ንጐይይ እምቅድመ ገጾሙ ።

፯ ወእምዝ እንከ ትትነሥኡ እንትሙሂ ወእኃዝዋ ለሀገሮሙ ወያገብኣ እግዚአብሔር አምላክክሙ ውስተ እዴክሙ ።

፰ ወእምከመ በእክምዋ ለሀገሮሙ አውዕይዋ በእሳት ወግበሩ በከመ እቤለክሙ ናሁ አዘዝኩክሙ ።

፱ ወፈነዎሙ ኢያሱ ወሐሩ ይዕግትዋ ለሀገር ወነበሩ ማእከለ ቤቴል ወማእከለ ጋይ እምባሕረ ጋይ ወቤተ ኢያሱ ሀየ በይእቲ ሌሊት ማእከለ ሕዝብ ።

፲ ወጌሠ በጽባሕ ወርእዮሙ ለሕዝብ ወዐርጉ ውእቱ ወሊቃውንቲሆሙ ለእስራኤል ፍጽመ ቅድመ ሕዝብ ላዕለ ጋይ ።

፲፩ ወዐርጉ ኵሎሙ ሕዝብ መስተቃትላን ምስሌሁ ወበጽሑ ወቀርቡ ቅድመ ሀገር እንተ መንገለ ጽባሒሃ ወዲኢቶ ማእከሎሙ ወማእከለ ጋይ ።

፲፪ ወነሥአ ኢያሱ ኃምስ ምእት ብእሴ ወአንበሮሙ ይዕግቱ ማእከለ ቤቴል ወማእከለ ጋይ መንገለ ባሕረ ጋይ ።

፲፫ ወአንበሩ ኵሉ ሕዝብ ተዓይኒሆሙ እንተ መንገለ መስዕ ለሀገር ወጽንፋ እስከ ባሕረ ሀገር ፡ ወሖረ ኢያሱ በይእቲ ዕለት ማእከለ ውእቱ ፂላት ።

፲፬ ወሶ ሰምዐ ንጉሠ ጋይ ጌሠ ፍጡነ ወወፅኡ ሰብአ ሀገር ወተቀበልዎሙ እንተ ቅድሜሆሙ ከመ ይትቃተልዎሙ ውእቱ ወኵሉ ሕዝብ ዘምስሌሁ በጊዜሃ መንጸረ ዐረባ ወኢያእመረ ውእቱሰ ከመ ዐገትዎሙ እንተ መንገለ ከዋላሃ ለሀገር ።

፲፭ ወሰበ በጽሕዎሙ ጐዩ ኢያሱ ወኵሉ እስራኤል እምቅድመ ገጾሙ ወነትዑ ውስተ ፍኖተ ገዳም ።

፲፮ ወኄሉ ኵሉ ሕዝበ ብሔር ወተለውዎሙ ወሰደድዎሙ ወዴገንዎሙ እምድኅሬሆሙ ለደቂቀ እስራኤል ።

፲፯ ወርኅቁሙ እሙንቱ እምሀገር አልቦ ዘተርፈ ወኢመኑሂ ውስተ ጋይ ወውስተ ቤቴል ዘኢተለዎሙ ወዘኢዴገኖሙ ለእስራኤል ወኀደግዋ ለሀገር ርኅውታ ።

፲፰ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለኢያሱ አልዕል እዴከ በጋይስ ዘውስተ እዴከ ላዕለ ጋይ እስመ ውስተ እዴከ አግብእክዋ ።

፲፱ ወእለሂ ዐገቱ ይትነሥኡ ፍጡነ እመካናቲሆሙ ፡ ወአልዐለ ኢያሱ እዴሁ በጋይሶ ላዕለ ሀገር ፡ ወእለሂ ዐገቱ ተንሥኡ ፍጡነ እመካናቲሆሙ ወወፅኡ ሶበ አልዐለ እዴሁ በጋይሶ ወበኡ ሀገረ ወአኀዝዋ ወአውዐይዋ ፍጡነ በእሳት ።

እንደምታውቁ ሄዳችሁ አገሪቱን በኋላዋ ከበቧት ፤ ከአገሪቱም ፈጽማችሁ አትራቁ ሁላችሁም የተዘጋጃችሁ ሁናችሁ ተደበቁ ብሎ አዘዛቸው ።

ከኔ ጋራ ያሉ ሕዝብ ሁሉና እኔ ግን ወደ ከተማይቱ እንቀርባለን ፤ ወጥተው በጦርነት በተቀበሉን ጊዜ እንደ ቀድሞአችን ከፊታቸው እንሸሻለን ። መሳ፡ ፳ ፴፪ ።

ወጥተው በተከተሉንም ጊዜ ከከተማይቱ እናርቃቸዋለን እነዚህም እንደ ቀድሞው ከፊታችን ሸሹ ይላሉ ፤ እኛም ከፊታቸው እንሸሻለን ። ኢያ፡ ፰ ፲፮ ።

ከዚህም በኋላ እናንተ ተነሥታችሁ አገራቸውን ያዟት ፈጣሪያችሁ እግዚአብሔርም በእጃችሁ ይጥላታል ። ኢያሱ ፩ ፲፮ ። ፪ [illegible] ፲፫ ፳ ።

አገራቸውንም ከገባችኋት በኋላ በእሳት አቃጥሏት ፤ እነሆ አዝዣችኋለሁ እንዳዘዝኋችሁም አድርጉ ።

ኢያሱም ላካቸው እነሱም አገሪቱን ይከቧት ዘንድ ሄዱ ፤ በጋይና በቤቴል መካከል በጋይ በምዕራብ በኩል ተቀመጡ ፤ ኢያሱም በዚያች ሌሊት በሕዝቡ መካከል አደረ ። ዘፍ፡ ፲፪ ፰ ፡ ፲፫ ፫ ።

ሲነጋም ገሥግሦ ሄዶ ሕዝቡን አያቸው የእስራኤል አለቆችና እሱ አስቀድመው በሠራዊቱ ፊት ወደ ጋይ ወጡ ። ዘፍ፡ ፳፪ ፫ ። መዝ፡ ፻፩ ፰ ። ኤር፡ ፳፭ ፲፪ ።

አርበኞች ወገኖች ሁሉ ከሱ ጋራ ወጡ ፤ በምሥራቅ በኩል ፊት ለፊት ደርሰው ቀረቡ ፤ በጋይና በእስራኤልም መካከል ዱር (ሸለቆ) ነበር ።

ኢያሱ አምስት ሺሕ ሰዎች ወስዶ ይከቡ ዘንድ በጋይና በቤቴል መካከል በጋይ ምዕራብ በኩል አኖራቸው ።

ሕዝቡ ሁሉ ሠራዊቶቻቸውን በአገሩ በቀኝ በኩል አኖሩ ዳርቻውም እስከአገሩ ምዕራብ ድረስ ነው ፤ ኢያሱም በዚያች ቀን በዱር መካከል ሄደ ። ዘፍ፡ ፴፱ ፲፱ ።

የጋይ ንጉሥም በሰማ ጊዜ ፈጥኖ ገሥግሦ ሄዶ ከርሱ ጋራ ያሉ ሠራዊቱ ሁሉና እሱም ወድያው በዐረባ አፍ ዘገር ሊዋጓቸው ወጥተው ያገሪቱ ሰዎች በፊታቸው ተቀበሏቸው እሱ ግን አገሪቱን በኋላዋ እንደ ከበቧት አላወቀም ነበር ። መሳ፡ ፳ ፴፬ ።

በደረሱባቸውም ጊዜ ኢያሱና እስራኤል ሁሉ ከፊታቸው ወደ ምድረ በዳው መንገድ ፈጽመው ሸሹ ።

በአገር ያሉም ሰዎች ዕልል አሉ፡ ተከትለውም አባረሯቸው የእስራኤልን ልጆች በኋላቸው ተከተሉዋቸው ።

እነዚያ ከገር በራቁ ጊዜ እስራኤልን ያልተከተላቸው በቤቴልና በጋይ ማንም ማን የቀረ አልነበረም ፤ አገሪቱን ከፍቷን ተዉዋት ።

እግዚአብሔር ኢያሱን በእጅህ ጥያታለሁና ፤ በእጅህ በያዝከው ጋሻ (ጦር) ወደ ጋይ ጥቀሳቸው አለው ።
ዘዳ፡ ፯ ፳፫ - ፳፬ ። ኢያሱ ፴፱ ፫ ።

የከበቡትም ሰዎች ከቦታቸው ፈጥነው ይነሡ አለው ፤ በእጁም በያዘው ጋሻ ወደ ጋይ ጠቀሳቸው ፤ በእጁም በያዘው ጋሻ በጠቀሳቸው ጊዜ የከበቡት ሰዎች ከቦታቸው ፈጥነው ተነሥተው ወጡ ፤ ወደ አገሪቱም ገብተው ያዙዋት ፤ ፈጥነውም በእሳት አቃጠሏት ።

፳ ወሶበ ነጸሩ ድኅሬሆሙ ሰብአ ጋይ ወርእዩ ጢሰ የዐ
ርግ ውስተ ሰማይ እምውስተ ሀገሮሙ ኀጥኡ እንከ ኀበ
ይጕይዩ ኢ ለፌ፡ ወኢ ለፌ ወሕዝብኒ እለ ጐዩ ውስተ
ገዳም ተመይጥዎሙ፡ ለእለ ዴገንዎሙ ።
፳፩ ወርእየ ኢያሱ ከመ ረከብዋ ለሀገር እለ ዐገትዋ ወእለ
መሩ ሰበ ርእዩ ጢሰ የዐርግ ውስተ ሰማይ እምሀገር ወእ
ምዝ ተመይጡ እስራኤል ወቀተልዎሙ ለሰብአ ጋይ ።
፳፪ ወእልክቱሂ ወፅኡ እምሀገር ወተቀበልዎሙ ወእግብ
እዎሙ ማእከለ ትዕይንቶሙ ለደቂቀ እስራኤል ወቀተል
ዎሙ ወእልክቱሂ እምከሐ ወእሉሂ እምለፌ እስከ ኢያት
ረፉ እምኔሆሙ ነፋጺተ ዘድኅነ ።
፳፫ ወአኀዝዎ ለንጉሠ ጋይ ሕያዎ ወወሰድዎ ኀበ ኢያሱ ።
፳፬ ወሶበ አኅለቁ ቀቲሎቶሙ ለሰብአ ጋይ በገዳም ወበ
ሙራደ ደብር በኀበ ዴገንዎሙ ወቀተልዎሙ ለኵሎሙ
በሐፂን ወአጥፍእዎሙ ተመይጠ ኢያሱ በጊዜሃ ውስተ
ጋይ ወቀተለ በሰይፍ ።
፳፭ ወኮኑ ኵሎሙ ሰብአ ጋይ እለ ሞቱ ይእተ አሚረ ተባ
ዕት ወአንስት እልፈ ወዕሥራ ምእተ ።
፳፮ ወኢሜጠ ኢያሱ እዴሁ እንተ አልዐለ በጋይሶ እስከ
አጥፍአሙ ለሰብአ ጋይ ።
፳፯ ዘእንበለ እንስሳ ወበርበረ ሀገር ኵሎ ዘበርበሩ ደቂቀ
እስራኤል ለርእሶሙ በከመ አዘዘ እግዚአብሔር ለኢያሱ ።
፳፰ ወአውዐያ ኢያሱ ለሀገር በእሳት ወኮነት ሐመደ ወረ
ሰያ ከመ አልቦ ዘይነብራ ለዝሉፉ እስከ ዛቲ ዕለት ።
፳፱ ወለንጉሠ ጋይ ሰቀሎ ዲበ ዕፀ ዘግብ ወነበረ ዲበ
ዕፅ እስከ ሠርክ ወሶበ ዐርበ ፀሐይ አዘዘ ኢያሱ ያው
ርድዎ፡ ወአውረድዎ እምዲበ ዕፅ ወወገርዎ ውስተ ግብ
ቅድመ እንቀጸ ሀገር ወአንበሩ ላዕሌሃ አእባነ ዐበይተ
እስከ ዛቲ ዕለት ።
፴ ወነደቀ ኢያሱ ምሥዋዐ ይእተ አሚረ ለእግዚአብሔር
አምላከ እስራኤል በደብረ ጌባል በከመ አዘዞሙ ሙሴ
ቍልዔሁ ለደቂቀ እስራኤል ።
፴፩ በከመ ጽሑፍ ውስተ ሕገ ሙሴ ምሥዋዐ ዘእብን በመ
ጥባሕት ዘኢተወቅረ ወዘኢተገብረ በሐፂን ወአዕረገ ቍር
ባነ ወመሥዋዕተ መድኃኒት ለእግዚአብሔር ።
፴፪ ወጸሐፎ ኢያሱ ውስተ እእባን ለዳግም ኦሪት ዘጸሐፈ
ሙሴ በቅድሜሆሙ ለኵሉ ደቂቀ እስራኤል ።
፴፫ ወኵሉ እስራኤል ወመኳንንቲሆሙ ወጸሐፍቶሙ ይቀ
ውሙ እምጸጋም ወእምየማን ቅድመ ታቦት ወካህናትሰ
ወሌዋውያን ይፀውሩ ታቦተ ሕጉ ለእግዚአብሔር ።
፴፬ ወመንፈቆሙ ለግዩራን ወእለሂ እምፍጥረቶሙ መንፈ
ቆሙ ጥቃ ደብረ ጌባል ወመንፈቆሙ ጥቃ ደብረ ገሪዝን
እለ አዘዞሙ ሙሴ ቍልዔሁ ለእግዚአብሔር ከመ ይባር

የጋይ ሰዎችም ወደ ኋላቸው ተመልሰው በዩ ጊዜ
ጢስ ከአገራቸው ወደ ሰማይ አቅንቶ ሲወጣ ተመለከቱ፡
ከዚያ በኋላ ወድያና ወዲህ የሚሸሹበትን አጡ ወደ ምድ
ረ በዳ የሸሹትም ወገኖች የተከተሏቸውን ሰዎች ተመለሱ
በቸው ። ኢያ፡ ፰ ፲፩ ፳፬፡ መሳ፡ ፲፭ ፲ ።
ኢያሱም የከበቧት ሰዎች አገሪቱን እንዳገኙዋት አየ፡
ከአገር ወደ ሰማይ ጢስ አቅንቶ ሲወጣ በዩ ጊዜ አገሬ
ቸው እንደ ተያዘች አወቀ፡ ከዚህ በኋላ እስራኤል ተመ
ልሰው የጋይን ሰዎች ወጉዋቸው ።
እነዚያም ከገር ወጥተው ተቀበሏቸው በእስራኤል ሰ
ፈር መከከል አግብተው ሸሽቶ የዳነውን የማያስቀሩ እስ
ኪሆኑ ድረስ እነያ ከወዲያ እነሀ ከወዲህ ሁነው ወጉዋቸው።
ዘሌዋ፡ ፳፯ ፳፱ ። ኢዮብ ፳ ፭ ።
የጋይን ንጉሥ ደኅነኛውን (ሳይሞት) ይዘው ወደ
ኢያሱ ወሰዱት ።
በተከተሏቸው ቍልቁለትና በምድረ በዳ የጋይን ሰ
ዎች መውጋት ከጨረሱ በኋላ ሁሉንም በጦር ወግተው
ከጠፉዋቸው በኋላ ኢያሱ ወድያው ወደ ጋይ ተመልሶ
በሰይፍ አጠፋቸው ።
ያን ጊዜ የሞቱ የጋይ ሰዎች ሴትና ወንድ ሁሉ አል
ፍ ከሁለት ሺሕ ሆኑ ።
ኢያሱም የጋይን ሰዎች እስኪያጠፋቸው ድረስ በጋ
ሻው የጠቀሰበት እጁን አላጠፈም (አልመለሰም) ።
እግዚአብሔር ለኢያሱ እንዳዘዘው የእስራኤል ልጆች
ለራሳቸው ከአገር ከዘረፉት ገንዘብ ሁሉና ከከብቱ በቀር
አልፍ ከሁለት ሺሕ ሆኑ ። ዘኍ፡ ፴፩ ፳፪ ፳፮ ።
ኢያሱም አገሪቱን በእሳት አቃጠላት፡ አመድም ሆነች
እስከዚችም ቀን ድረስ ለዘለዓለሙ የሚኖርበት እንዳይኖር
አደረጋት ። ዘዳ፡ ፲፫ ፲፮ ።
የጋይንም ንጉሥ በዝግባ ዕንጨት ላይ ሰቅለው እስከ
ሠርክ ድረስ በዕንጨት ላይ ተሰቅሎ ዋለ፡ ፀሐይ ከገባ
በኋላም ኢያሱ ያወርዱት ዘንድ አዘዘ፡ ከዕንጨት ላይ
አውርደው በአገሩ አደባባይ ፊት ለፊት ባለ ጕድጓድ ው
ስጥ ጣሉት እስከዚችም ቀን ድረስ ታላላቅ ደንጊያዎችን
በጕድጓዱ አፍ ገጠሙት ። ኢያ፡ ፯ ፳፮ ።
ያን ጊዜ ኢያሱ ጌባል በሚባል ተራራ ለእስራኤል
ፈጣሪ ለእግዚአብሔር መሠውያን ሠራ፡ የእግዚአብሔር
ባለሟል ሙሴ የእስራኤልን ልጆች እንዳዘዛቸው ።
በሙሴ መጽሐፍ በዳግም ሕግ እንደ ተጻፈ በመጥረ
ቢያ ባልተጠረበ በብረትም ባልተቀረጸ መሠውያ ላይ የድ
ኅነት መሥዋዕትንና ቍርባንን ለእግዚአብሔር አቀረበ ።
ሙሴ በእስራኤል ልጆች ሁሉ ፊት የጻፈው ዳግም
ሕግን ኢያሱ በደንጊያዎች ላይ ጻፈው ። ዘዳ፡ ፳፯ ፳፰ ።
መኳንንቱና እስራኤል ሁሉ ሹማምንቱም በታቦት ፊት
በቀኝ በግራ ቆመው ነበር፡ የሌዊ ወገኖችና ካህናቱ ግን
የእግዚአብሔር የሕጉ ማደሪያ ታቦትን ተሸክመው ነበር ።
የእስራኤልን ወገኖች ይመርቁዋቸው ዘንድ የእግዚአ
ብሔር ወዳጅ ሙሴ ያዘዛቸው ከመጻተኞችም ፍጥረታ
ቸው ከእስራኤል የሆኑትም ወገን እኩሌታዎች በጌባል

ክዎሙ ለሕዝበ እስራኤል ወእሙንቱ ይቀድሙ ።

አጠገብ እኩሌታዎች በገሪዛን አጠገብ ቆመው ነበር ።

፴፬ ወእምድኅረ ዝንቱ አንበበ ኢያሱ ኵሎ ነገሮ ለዝንቱ ሕግ በረከቶሂ ወመርገሞሂ ኵሎ ዘጽሑፍ ውስተ ዝንቱ ሕገ ሙሴ ።

ከዚህ በኋላ ኢያሱ የዚህን የዳግም ሕግን ነገር ሁሉ በረከቱንም መርገሙንም አነበበላቸው ፤ በሙሴ መጽሐፍ በዳግም ሕግ የተጻፈውን ሁሉ ። ዘዳ፡ ፴፩ ፲፩ ።

፴፭ ወአልቦ ቃል እምኵሉ ዘአዘዘ ሙሴ ለኢያሱ ዘኢያንበበ ወዘኢያሰምዖሙ ኢያሱ ለኵሉ ተዓይነ ደቂቀ እስራኤል ለእደዊሆሙ ወለአንስትያሆሙ ወለደቂቆሙ ወለግዩራን እለ ሖሩ ምስሌሆሙ ።

ሙሴ ለኢያሱ ካዘዘው ሁሉ ፤ ኢያሱ ለእስራኤል ልጆች ወገን ሁሉ ለሴቶችና ለወንዶች ከእስራኤል ጋራ ለሄዱት መጻተኞችና ለልጆቻቸውም ያላሰማቸውና ያላነበበላቸው ቃል የለም ። ዘዳ፡ ፴፩ ፲፪ ፤ ኢያ፡ ፳ ፴፪ ።

## ምዕራፍ ፱ ።

፩ ወሶበ ሰምዑ ኵሎሙ ነገሥተ አሞሬዎን እለ ሀለዉ ማዕዶተ ዮርዳኖስ እለ ውስተ አድባር ወእለ ውስተ ገዳም ወእለ ውስተ ኵሉ ሐይቀ ባሕር ዐቢይ ወእለ ውስተ አንጢሊባኖን ወኬጤዎን ወከናኔዎን ወፌርዜዎን ወኤዌዎን ወአሞሬዎን ወጌርጌሴዎን ወኢያቡሴዎን ተጋብኡ ኅቡረ ከመ ይፅብእዎሙ ለኢያሱ ወለኵሉ እስራኤል ።

በዮርዳኖስ ማዶ በቈላው በደጋው በታላቁ በሕር ዳር ያሉ የአሞሬዎን ነገሥታት ሁሉ በሊባኖስም አቅራቢያ የሚኖሩ የኬጤዎን የከናኔዎን የፌርዜዎን የኤዌዎን የአሞሬዎን የጌርጌሴዎንና የኢያቡሴዎን ሰዎች የእስራኤልን መምጣት በሰሙ ጊዜ ኢያሱንና እስራኤልን ሁሉ ለመውጋት አንድነት ተሰበሰቡ ። ዘዳ፡ ፩ ፯ ፤ ኢያ፡ ፲፪ ፰ ።

፪ ወሰምዑ እለ ይነብሩ ውስተ ገባኦን ኵሎ ዘገብረ እግዚአብሔር ላዕለ ኢያሪኮ ወላዕለ ጋይ ።

በገባኦን የሚኖሩ ሰዎች እግዚአብሔር በኢያሪኮና በጋይ ያደረገውን ሁሉ ሰሙ ። ኢያ፡ ፲፪ ፲፪ ።

፫ ወገብሩ እሙንቱሂ በጕሕሉት ወመጽኡ ሰኰቆሙ ወአስተዳሊዎሙ ወፆሩ መሰንቆቲሆሙ ብሉያተ ዲበ መቻክፍቲሆሙ ወዝቃተ ወይን ብሉያተ ወሥጡጣተ ወጥቁባተ ።

እነሱም ተንኰል አድርገው መጡ ፤ ስንቃቸውን ሰንቀው አዘጋጅተው ያረጁ አቁማዳዎቻቸውን በትከሻቻቸው ተሸክመው ተቀደው የተጠቀሙና ያረጁ የወይን ረዋቶችን ።

፬ ወብቱክ ቶታነ ሰኳእኒሆሙ ወብሉይ እሣእኒሆሙ ወግቱት ውስተ እገሪሆሙ ወአልባሲሆሙኒ ብሉይ በላዕሌሆሙ ወኅብስተ ስንቆሙኒ ይቡስ ወስሑብ ።

የጫማዎቻቸው ማዘቢያ ተቈርጦ ጫማቸው አርጅቶ በእግሮቻቸው ማትቻ ሆኖ በላያቸውም ላይ ልብሳቸው ያረጀ ሆኖ የስንቃቸውም እምባሻ ደርቆ ሻግቶ ።

፭ ወመጽኡ ኀበ ኢያሱ ወኀበ እስራኤል ውስተ ገልገላ ወይቤልዎሙ ለኢያሱ ወለኵሉ እስራኤል እምርኁቅ ብሔር መጻእነ ወይእዜኒ ተማሐሉ ምስሌነ ።

ከኢያሱና ከእስራኤል ዘንድ ወደ ገልገላ መጥተው ለኢያሱና ለእስራኤል ልጆች ሁሉ እኛ ከሩቅ አገር መጥተናል አሁንም ከኛ ጋራ ተማማሉ አሏቸው ።

፮ ወይቤልዎሙ ደቂቀ እስራኤል ለኤዎዋውያን እፎ ንትማሐል ምስሌከሙ መሐላ ሀቁ ዮጊ ቅሩባኒ ትነብሩ ።

የእስራኤልም ልጆች የኤዌዎንን (የገባኦን) ከናንተ ጋራ እንዴት መሐላ እንማማላለን ፤ አሁንም በአቅራቢያችን ትኖሩ እንደሁ ዕወቁ አሉዋቸው ።

፯ ወይቤልዎ ለኢያሱ ንሕነሰ አግብርቲከ እምርኁቅ ብሔር ንሕነ ፤ ወይቤሎሙ እምአይቴ አንትሙ ወእምአይቴ መጻእክሙ ።

ኢያሱን እኛ ከሩቅ አገር የመጣን ባሮችህ ነን አሉት እርሱም ከወዴት ናችሁ ፤ ከወዴትስ አገር መጣችሁ ፤ አላቸው ። ኢያ፡ ፱ ፲፩ ፤ ፪ ነገ፡ ፲ ፭ ።

፰ ወይቤልዎ እምርኁቅ ብሔር ጥቀ መጻእነ ንሕነ አግብርቲከ በስመ እግዚአብሔር አምላክከ እስመ ሰማዕነ ዘበእንቲአሁ ኵሎ ዘገብረ በግብጻውያን ።

እነሱም እኛ ባሮችህ በፈጣሪህ በእግዚአብሔር ስም አምነን እጅግ ከሩቅ አገር መጥተናል ፤ በግብጻውያን ላይ ያደረገውን ሁሉ ። ኢያ፡ ፪ ፲ ፤ ፯ ፳፯ ።

፱ ወኵሎ ዘገብረ በክልኤቱ ነገሥተ አሞሬዎን እለ ይነብሩ ውስተ ማዕዶተ ዮርዳኖስ ፤ በሴዎን ንጉሠ ሐሴቦን ፤ ወበዖግ ንጉሠ ባሳን ዘይነብር ውስተ አስጣሮት ወውስተ ኤንድራይን ።

በዮርዳኖስ ማዶ በሚኖሩ በሁለቱ በአሞሬዎን ነገሥታት በኤንድራይንና በአስጣሮት በሚኖሩ በባሳን ንጉሥ በዓግና በሐሴቦን ንጉሥ በሴዎን ያደረገውን ሁሉ ሰምተን መጥተናል አሉት ። ዘኁ፡ ፳ ፳፭ ፤ ፳ ፲፭ ።

፲ ወይቤሉነ ሊቃናቲነ ወኵሉ ሰብአ ብሔርነ ንሥኡ ስንቀ ለፍኖት ወሖሩ ትትቀበልዎሙ ወበልዎሙ አግብርቲክሙ ንሕነ ወይእዜኒ ተማሐሉ ምስሌነ ።

የአገራችን ሰዎች ሁሉና አለቆቻችን ትቀበሏቸው ዘንድ እንግዲህ ለመንገዳችሁ ስንቅ ይዛችሁ ሂዱ እኛ ባሮቻችሁ ነን አሁንም ከኛ ጋር ተማማሉ በሉዋችሁ አሉን ።

፲፩ ወናሁ ዝንቱ ኅብስትነ እንዘ ምውቅ ውእቱ ነሣእናሁ እምአብያቲነ በዕለተ ወፃእነ ከመ ንምፃእ ኀቤክሙ ወይእዜሰ ነቅዘ ወየብሰ ።

እነሆ ይህ እምባሻችን ወደናንተ እንመጣ ዘንድ ከቤታችን በወጣንበት ቀን ትኩሱን የያዝነው አሁን ግን ሻገተ ደረቀ ።

፲፫ ወዝንቱኒ ዝቅ ወይን ዘመላእናሁ ሐዲስ ይእዜሰ ወርቀ
ወበልየ ወተሠጠ ፡ ወዝንቱ አልባሲነ ወአሣእኒነኒ በልየ
እስመ ጥቀ ርኁቅ ፍኖትነ ።

፲፬ ወነሥኡ መኳንንት ስንቆሙ ወኢተስእሉ በኀበ እግ
ዚአብሔር ።

፲፭ ወገብረ ኢያሱ ሰላመ ምስሌሆሙ ወተማሐለ ምስሌ
ሆሙ ከመ ያድኅኖሙ ወመሐሉ ሎሙ መላእክተ ተዓይን ።

፲፮ ወእምድኅረ ሠሉስ መዋዕል እምድኅረ ተማሐሉ ምስ
ሌሆሙ መሐላ ሰምዑ ከመ እምቅሩብ እሙንቱ ወከመ
ኀቤሆሙ እሙንቱ ይነብሩ ።

፲፯ ወግዕዙ ደቂቀ እስራኤል ወበጽሑ ውስተ አህጉሪ
ሆሙ አመ ሣልስት ዕለት ወእላንቱ እማንቱ አህጉሪሆሙ
ገባኦን ፡ ወፌፌ ፡ (ፋፌ) ወቤሮት ፡ ወኢያርም ።

፲፰ ወኢቀተልዎሙ ደቂቀ እስራኤል እስመ መሐሉ ሎሙ
ኵሎሙ መላእክተ ተዓይን በእግዚአብሔር አምላከ እስራ
ኤል ወኢንጐርጐሩ ኵሉ ተዓይኒሆሙ ሰደቂቀ እስራኤል
ላዕለ ኵሉ መላእክቲሆሙ ።

፲፱ ወይቤልዎሙ ኵሉ መላእክት ለኵሉ ተዓይን ንሕነ
መሐልነ ሎሙ በእግዚአብሔር አምላከ እስራኤል ወይእ
ዜኒ ኢንክል ለኪፎቶሙ ወኢበምንትኒ ።

፳ ወከመዝ ባሕቱ ንግበር ናሕይዎሙ ወንቅንዮሙ ወኢ
ይከውን ላዕሌነ መንሱት በበይነ ዘመሐልነ ሎሙ ።

፳፩ ወይቤልዎሙ መላእክት አሕየውናክሙ ወሜምናክሙ
ትሕጥቡ ዕፀወ ፡ ወትቀድሑ ማየ ፡ ለኵሉ ተዓይን ፡ ወከ
መዝ አዘዝዎሙ መላእክት ።

፳፪ ወጸውዖሙ ኢያሱ ወይቤሎሙ ለምንት ተሣለቅሙ
ላዕሌነ ወትቤሉነ ርኁቃን ንሕነ ጥቀ እምኔክሙ ፡ ወናሁ
አንትሙ ትነብሩ ውስቴትነ ።

፳፫ ወይእዜኒ ርጉማን ኮኑ ወኢይሰዐር እምኔክሙ ገብር
ዘየሐጥብ ዕፀ ወዘይቀድሕ ማየ ለአምላኪየ ወሊተኒ ።

፳፬ ወአውሥእዎ ወይቤልዎ ዜና ዜነዉነ ኵሎ ዘይቤሎ
እግዚአብሔር አምላክከ ለሙሴ ቍልዔሁ ከመ የሀብክሙ
ዘተ ምድረ ወከመ ያጥፍአነ ለነ ወለኵሎሙ እለ ይነብሩ
ውስቴታ እምቅድመ ገጽክሙ ወበበይነዝ ገበርነ ዘንተ
ነገረ ።

፳፭ ወይእዜኒ ናሁ ንሕነ ውስተ እዴክሙ ዘከመ ፈቀድ
ክሙ ወዘከመ ይኤድመክሙ ትረስዩነ ረስዩነ ።

፳፮ ወአድኀኖሙ ኢያሱ በይእቲ ዕለት ወረሰዮሙ ሐጣ
ብያነ ዕፀው ወሐዋርያነ ማይ ለምሥዋዐ እግዚአብሔር
ወለኵሉ ተዓይን ።

፳፯ ወበበይነ ዝንቱ ኮኑ ሰብአ ገባኦን ሐጣብያነ ዕፀው ፡
ወሐዋርያነ ማይ ለኵሉ ተዓይን ወለምሥዋዐ እግዚአብ
ሔር እስከ ዛቲ ዕለት ።

ምዕራፍ ፲ ።

፩ ወሰበ ሰምዐ አዶኒቤዜቅ ንጉሠ ኢየሩሳሌም ከመ ነሥ
አ ኢያሱ ለጋይ ወአጥፍአ በከመ ገብራ ለኢያሪኮ ወለን
ጉሣ ወከመ ለሲሆሙ ሐሩ ሰብአ ገባኦን ኀበ ኢያሱ ወኀበ

ይህም የወይናችን ረዋት አዲሱን መላነው አሁን ግን
ተራቁተ አርጅቶም ተቀደደ ፡ መንገዳችን እጅግ የራቀ
ነውና ይህም ልብሳችን አዲሱን ለብሰነው ፡ ይህም ጫማ
ችን አዲሱን ተጫምተነው አረጀ በሲቸው አሉን አሉት ።

መኳንንቱም ስንቃቸውን ተቀብለው አዩ ፡ የእግዚአ
ብሔርንም ቃል አልጠየቁም ። ዘኍ ፳፯ ፳፩ ።

ኢያሱም ከነሱ ጋራ ዕርቅ አድርጎ ያድናቸው ዘንድ
ከነሱ ጋር ተማማለ ፡ የሕዝቡም አለቆች ማሉላቸው ።

ከነሱ ጋር መሐላን ከተማማሉ ከሦስት ቀን በኋላ ከቅ
ርብ (ጐረቤታቸው) እንደሆኑ እነዚያም በአጠገባቸው እን
ደሚኖሩ ሰሙ ።

የእስራኤልም ልጆች ተጕዘው በሦስተኛው ቀን ወደ
አገራቸው ደረሱ ፡ እነዚያም አገሮች ገባኦን ፋራን ቤሮት
ኢያርም ናቸው ። ኢያ፡ ፲፰ ፳፭ ። ሕዝ፡ ፪ ፳፭ ።

የሕዝቡም አለቆች ሁሉ በእስራኤል ፈጣሪ ስም ምለ
ውላቸዋልና የእስራኤል ልጆች አልወጉዋቸውም ፡ የእስ
ራኤል ልጆች ወገኖችም ሁሉ በአለቆቻቸው ሁሉ ላይ
አንጐራጐሩ ።

አለቆቻቸውም ሁሉ ሕዝቡን ሁሉ እኛ በእስራኤል
ፈጣሪ በእግዚአብሔር ስም ምለንላቸዋል ፡ አሁንም ምን
ም ምን ልንነካቸው አንችልም አሉዋቸው ።

ነገር ግን እንዲህ እናድርግ ፡ ስለ ማልንላቸው አድነን
እንግዛቸው ስለ ማልንላቸውም መቅሠፍት አይደረግብንም ፤

አለቆቹም ለሰፈሩ ሁሉ ውኃ እንዲቀዱ ፡ ዕንጨት
እንዲሰበስቡ አድነን አኖርናችሁ አለቆቹ እንዲህ አድር
ገው አዘዟቸው ። ኢያ፡ ፱ ፳፫ ፡ ፱ ፲፭ ።

ኢያሱም ጠርቶ ከናንተ እጅግ የራቅን ነን ብላችሁ
ለምን ዘበታችሁብን እነሆ እናንተ በጠገባችን ትኖራላችሁ
እንዲህ ስትሆኑ ለምን ዘበታችሁብን ፤ አላቸው ።

አሁንም የተረገማችሁ ሁኑ ለኔና ለፈጣሪዬ ውኃ የሚቀ
ዳና ዕንጨት የሚሰብር አገልጋይ ከናንተ አይታጣ አላቸው።

እነሱም እንዲህ ብለው መለሱለት ፡ ይህችን ምድር
ይሰጣችሁ ዘንድ እኛንም ያጠፋን ዘንድ በውስጧ የሚ
ኖሩ ሰዎችንም ሁሉ ከፊታችሁ ያጠፋቸው ዘንድ ፈጣሪህ
እግዚአብሔር ለወዳጁ ለሙሴ የነገረውን ነገር ሁሉ ነገሩን
ስለዚህ ይህን ነገር አደረግን ። ዘፀ፡ ፲፭ ፲፬ ።

አሁንም እነሆ እኛ በእጃችሁ ነን እንደ ወደዳችሁ ደስ
እንደሚላችሁም ታደርጉን ዘንድ አድርጉን አሉት ።

ኢያሱም በዚያች ቀን አዳናቸው ለሰፈሩ ሁሉና ለእ
ግዚአብሔርም መሠውያ ውኃ ቀጅና ዕንጨት ሰባሪ አደ
ረጋቸው ። ፩ ዜና መ፡ ፱ ፪ ። ዕዝ፡ ፪ ፵፫ ።

ስለዚህም ነገር የገባኦን ሰዎች ለሰፈሩ ሁሉና ለእ
ግዚአብሔር መሠውያ ዕንጨት ሰባሪዎችና ውኃ ቀጂ
ዎች ሆኑ ።

ምዕራፍ ፲ ።

የኢየሩሳሌም ንጉሥ አዶንቤዜቅ ፡ ኢያሱ ኢያሪኮን
እንዳጠፋት ንጉሧንም እንዳጠፋው ፡ ጋይንም እንደ
አደረጋት የገባኦን ሰዎችም ወደ እስራኤልና ወደ ኢያሱ

፲፬ ወአቴር ወሙፋራታሃ ፡ ወኤታም ወሙፋራቲሃ ።

አቴር ከመሠማሪያዋ ጋራ ኤታም ከመሠማሪያዋ ጋራ ።

፲፭ ወሄሎን ወሙፋራቲሃ ፡ ወዳቤር ወሙፋራቲሃ ።

ሄሎን ከመሠማሪያዎቿ ጋራ ፡ ዳቤር ከመሠማሪያዎቿ ጋራ ። ኢያ፡ ፲ ፴፫ ፡ ፲፭ ፲፮ ። ፩ ዜና መ፡ ፮ ፶፰ ።

፲፮ ወናሰን ወሙፋራቲሃ ፡ ወዩጣ ወሙፋራቲሃ ፡ ወቤተ ሳሚስ ወሙፋራቲሃ ፡ ተስዑ አህጉር እምክልኤቱ ሕዝብ።

ናሰን ከመሠማሪያዎቿ ጋራ ፡ ዩጣ ከመሠማሪያዎቿ ጋራ ቤተ ሳሚስ ከመሠማሪያዎቿ ጋራ ፡ ከነዚህ ከሁለቱ ነገድ የተሰጡ እነዚህ ዘጠኝ አገሮች ናቸው ። ኢያ፡ ፲፭ ፶፪ ።

፲፯ ወእምነገደ ብንያም ገበአን ወሙፋራቲሃ ፡ ወጋማላቄ ወሙፋራቲሃ ።

ከነገደ ብንያም የተሰጡ አገሮች ገባዖን ከመሠማሪያዎቿ ጋራ ፡ ጋማላቄ ከመሠማሪያዎቿ ጋራ ።

፲፰ ወአናቶት ወሙፋራቲሃ ፡ ወአሌሞን ወሙፋራቲሃ አርባዕቱ አህጉር ።

አናቶት ከመሠማሪያዎቿ ጋራ ፡ አሌሞን ከመሠማሪያዎቿ ጋራ ፡ እነዚህ አራቱ አገሮች ናቸው ።

፲፱ ወኵሎሙ አህጉሪሆሙ ለደቂቀ አሮን ክህናት በሥሩ ወሠላስ አህጉር ፡ ወሙፋራቲሃ ከማሁ ።

አገልጋዮች የሆኑ የአሮን ልጆች አገሮች ሁሉ ዓሥራ ሦስት ናቸው ፡ ከመሠማሪያዎቻቸው እንደዚያው ናቸው።

፳ ወለደቂቀ ቀዓት ሌዋውያን ፡ እለ ተርፉ ከና አህጉሪሆሙ እምሕዝበ ኤፍሬም ፡ ወወሀቦሙ ሀገረ ምስከይ ለቀታሊ ።

ለቀሩት ለቀዓት ልጆች ለሌዋውያንም አገሮቻቸው ከኤፍሬም ወገን ዕጣ ሆኑ ፡ ነፍስ ለገደለ ሰው መማጠኛ ሊሆን መማጠኛ አገር ሰጣቸው ።

፳፩ ሴኬም ወሙፋራቲሃ ፡ ወቤቶሮን ወሙፋራቲሃ ፡ ጌዜር ወሙፋራቲሃ ፡ ወቄቤጼይ ወሙፋራቲሃ ፡ አርባዕ አህጉር ።

ሴኬም ከመሠማሪያዎቿ ጋራ ፡ ቤቶሮን ከመሠማሪያዎቿ ጋራ ፡ ጌዜር ከመሠማሪያዎቿ ጋራ ፡ ቄቤጼይ ከመሠማሪያዎቿ ጋራ እነዚህ አራት አገሮች ናቸው ።

፳፪ ወእምሕዝበ ዳን ኤሊቴቁም ወሙፋራቲሃ ፡ ወገባቶን ወሙፋራቲሃ ።

ከነገደ ዳን ዕጣም ኤሊቴቁም ከመሠማሪያዎቿ ጋራ ፡ ገባቶን ከመሠማሪያዋ ጋራ ። ኢያ፡ ፲፱ ፵፬ ።

፳፫ ወኤሎን ወሙፋራቲሃ ፡ ወጌቴርምን ወሙፋራቲሃ ፡ አርባዕ አህጉር ።

ኤሎን ከመሠማሪያዋ ጋራ ፡ ጌቴርምን ከመሠማሪያዋ ጋራ ፡ (ከነገደ ዳን) የተሰጡ እሊህ ዓራት አገሮች ናቸው።

፳፬ ወእመንፈቀ ነገደ ምናሴ ጠናሕ ወሙፋራቲሃ ፡ ወዮብት ወሙፋራቲሃ ፡ ክልኤቲ አህጉር ።

ከነገደ ምናሴ እኩሌታ ዕጣ የተለዩ (የተሰጡ) አገሮች ጠናሕ ከመሠማሪያዋ ጋራ ፡ ዮብታም ከመሠማሪያዋ ጋራ እነዚህ ሁለቱ አገሮች ናቸው ። መሳ፡ ፩ ፲፱ ።

፳፭ ወኵሎን አህጉር በሥሩ ወሙፋራቲሆን ዘቅሩበን ለነገደ ደቂቀ ቀዓት እለ ተርፉ ።

ለቀሩት ለቀዓት ልጆች ነገድ አቅራቢያዎች የሚሆኑ ከመሠማሪያዎች ጋራ የተሰጡ አገሮች ሁሉ ዓሥር ናቸው።

፳፮ ወለደቂቀ ጌድሶን ሌዋውያን እመንፈቀ ነገደ ምናሴ አህጉር እለ ፈለጡ ምስከየ ለቀታሊ ፡ ጋውሎን በባሳን ፡ ወሙፋራቲሃ ፡ ወአስጣሮት በባሰር ወሙፋራቲሃ ፡ ክልኤቲ አህጉር ።

ለካህናት ለሆኑ ለጌድሶን ልጆችም ለነፍሰ ገዳይ መማጠኛ ሊሆኑ ከምናሴ ነገድ እኩሌታ የተለዩ አገሮች ከመሠማሪያዋ ጋራ በባሳን ያለች ጋውሎን ፡ በበሰር ያለች አስጣሮት ከመሠማሪያዋ ጋራ እነዚህ ሁለቱ አገሮች ናቸው ። ኢያ፡ ፳፩ ፮ - ፳፫ ። ፩ ዜና መ፡ ፮ ፸፩ ።

፳፯ ወእምነገደ እሴር መሴላ ወሙፋራቲሃ ፡ ወአቤጾን ወሙፋራቲሃ ፡ ወያቃቅ ወሙፋራቲሃ ፡ ወሮዓብ ወሙፋራቲሃ ፡ አርባዕ አህጉር ።

ከነገደ አሴር ዕጣ የተለዩም አገሮች መሴላ ከመሠማሪያዋ ጋራ ፡ አቤጾን ከመሠማሪያዋ ጋራ ፡ ያቃቅ ከመሠማሪያዋ ጋራ ፡ ሮዓብ ከመሠማሪያዋ ጋራ እነዚህ አራቱ አገሮች ናቸው ።

፳፰ ወእምነገደ ይሳኮር ቂሶዮን ወዳቤራት ወሙፋራቲሆን ያሬማት ወኤንጋን ወሙፋራቲሆን ፡ አርባዕ አህጉር ።

ከነገደ ይሳኮር ዕጣ የተለዩም አገሮች ዳቤራታና ቂስዮን ከመሠማሪያዎቻቸው ጋራ ፡ ያሬማትና ኤንጋን ከመሠማሪያዎቻቸው ጋራ እነዚህ አራቱ አገሮች ናቸው ።

፳፱ ወእምሕዝበ ንፍታሌም ሀገር ዘፈለጡ ለቀታሊ ቃዴስ በገሊላ ወሙፋራቲሃ ፡ ወኤማት ወሙፋራቲሃ ፡ ወቀርያቲአም ወሙፋራቲሃ ፡ ሠላስ አህጉር ።

ለነፍሰ ገዳይ መማጠኛ ሊሆኑ ከንፍታሌም ወገን ዕጣ የለዩዋቸውም አገሮች በገሊላ ያለች ቃዴስ ከመሠማሪያዋ ጋራ ኤማት ከመሠማሪያዋ ጋራ ፡ ቀርያቲአም ከመሠማሪያዋ ጋራ እነዚህ ሦስቱ አገሮች ናቸው ።

፴ ወኵሎን አህጉር ዘጌድሶን በበሕዘቢሆሙ ዓሥሩ ወሠላስ አህጉር ።

በየወገኖቻቸው የጌድሶን ልጆች የተቀበሉዋቸው አገሮች ሁሉ ዓሥራ ሦስት አገሮች ናቸው ።

፴፩ ወለነገደ ሕዝበ ሜራሪ እለ ተርፉ እምሌዋውያን እምሕዝበ ዛብሎን ፡ ኢያቅማን ወሙፋራቲሃ ፡ ወቃዴስ ወሙፋራቲሃ ።

ከሌዋውያን ለቀሩ ለሜራሪ ወገኖች ከዛብሎን ወገኖች ዕጣ የተሰጡ አገሮች ኢያቅማን ከመሠማሪያዋ ጋራ ቃዴስ ከመሠማሪያዋ ጋራ ።

፴፮ ወሲላ ወመሓፍሪቲሃ፤ ሚጌታኒ ወመሓፍሪቲሃ፣ አርባዕ አህጉር ።

፴፯ ወበማዕዶተ ዮርዳኖስ ዘመንገለ ኢያሪኮ እምሕዝበ ሮቤል ሀገረ ምስካይ ለቃታሊ፣ ባሶር በገዳም ወመሓፍሪቲሃ ።

፴፰ ወያዜር ወመሓፍሪቲሃ፣ ወቄዴሞት ወመሓፍሪቲሃ፣ ወሜፌአት ወመሓፍሪቲሃ፣ አርባዕ አህጉር ።

፴፱ ወእምሕዝበ ጋድ ሀገር ለምስካየ ቀታሊ ሬሞት በገለዓድ ወመሓፍሪቲሃ፣ ወምናኤም ወመሓፍሪቲሃ ።

፵ ወሐሴቦን ወመሓፍሪቲሃ፣ ወኢያኔዜር ወመሓፍሪቲሃ አርባዕ አህጉር ።

፵፩ ወኵሉ አህጉሪሆሙ ለእለ ተርፉ እምነገደ ሌዊ ለደቂቀ ሜራሪ በበነገዶሙ፣ ወኮነ ደወሎሙ አሠሩ ወክልኤቱ አህጉር ።

፵፪ ወኵሉ አህጉሪሆሙ ለሌዋውያን በማእከለ ደወሎሙ ለደቂቀ እስራኤል አርባዓ ወሰማኒ አህጉር ወመሓፍሪቲሆን፣ ዘዓውዶን ለእማንቱ አህጉር ።

፵፫ ለለሀገር ወመሓፍሪቲሃ፣ ዓውዳ ለሀገር ከማሁ ለኵሎን እላንቱ አህጉር ።

፵፬ ወፈጸመ ኢያሱ ከፊለ ምድር በበደወሎሙ፣ ወወሀቦሙ እግዚአብሔር ለደቂቀ እስራኤል ኵሎ ምድረ ዘመሐለ ለአበዊሆሙ፣ ወተዋረስዋ ወነበሩ ውስቴታ ።

፵፭ ወአዕረፎሙ እግዚአብሔር እምኦለ ዓውዶሙ በከመ መሐለ ለአበዊሆሙ፣ ወአልቦ እንከ መኑሂ ዘተቃወሞሙ ቅድመ ገጾሙ እምኵሉ ፀሮሙ፣ እስመ አግብኦሙ እግዚአብሔር ለኵሎሙ ፀሮሙ ውስተ እደዊሆሙ ።

፵፮ ወኢተርፈት አሐቲኒ ቃል እምኵሉ ሠናያት ዘይቤሎሙ እግዚአብሔር ለደቂቀ እስራኤል ኵሉ በጽሐሙ ።

## ምዕራፍ ፳፪ ።

፩ ወእምዝ ጸውዖሙ ኢያሱ ለደቂቀ ሮቤል ወለደቂቀ ጋድ ወለመንፈቀ ነገደ ምናሴ ።

፪ ወይቤሎሙ ለሊክሙ ሰማዕክሙ ኵሎ ዘአዘዘክሙ ሙሴ ቍልዔሁ ለእግዚአብሔር ወሰማዕክሙ ቃልየ ኵሎ ዘአዘዝኩክሙ ።

፫ ወኢኀደግሙ አኃዊክሙ በእማንቱ መዋዕል ብዙኃት እስከ ዛቲ ዕለት ወሀቀብክሙ ትእዛዘ ለእግዚአብሔር አምላክክሙ ።

፬ ወይእዜሰ አዕረፎሙ እግዚአብሔር አምላክክሙ ለአኃዊክሙ በከመ ይቤሎሙ ።

፭ ወይእዜኒ ተመየጡ ወእትዉ ውስተ አብያቲክሙ ወውስተ ይወልክሙ ውስተ ብሔር ዘወሀበክሙ ሙሴ ገብረ እግዚአብሔር በማዕዶተ ዮርዳኖስ ።

፮ ወባሕቱ ተዓቀቡ ከመ ትግበሩ ጥቀ ትእዛዘ ወሕገ ዘአዘዘክሙ ሙሴ ቍልዔሁ ለእግዚአብሔር ከመ ታፍቅርዎ ለእግዚአብሔር አምላክነ ወትሑሩ በኵሉ ፍናዊሁ ወት

ሲላ ከመሠማሪያዋ ጋራ፣ ሚጌታኒ ከመሠማሪያዋ ጋራ እነዚህ አራት አገሮች ናቸው ። ኢያ፡ ፲፱ ፴፯ ።

በኢያሪኮ አንጻር ባለች ከዮርዳኖስ ማዶ ለነፍስ ገዳይ መማጠኛ ሊሆኑ ለሮቤል ወገኖች ለጣ የተለዩ አገሮች በምድረ በዳ ያለች ባሶር ከመሠማሪያዋ ጋራ ።

ያዜር ከመሠማሪያዋ ጋራ፣ ቄዴሞት ከመሠማሪያዋ ጋራ ሜፋአት ከመሠማሪያዋ ጋር እነዚህ አራት አገሮች ናቸው ። ኢያ፡ ፳፰፣ ፲፫-፲፰ ።

ለነፍሰ ገዳይ መማጠኛ ሊሆኑ ለጋድ ወገኖች የተለዩ አገሮችም በገለዓድ ያለች ሬሞት ከመሠማሪያዋ ጋራ፣ ምናኤም ከመሠማሪያዋ ጋራ ። ፩ ነገ፡ ፳፪ ፫።

ሐሴቦን ከመሠማሪያዋ ጋራ፣ ኢያኔዜር ከመሠማሪያዋ ጋራ፣ እነዚህ አራት አገሮች ናቸው ።

ከነገደ ሌዊ ለቀሩ ለሜራሪ ልጆች በየነገዳቸው የደረሷቸው አገሮች ሁሉ እነዚህ ናቸው፤ አውራጃዎቻቸውም ዓሥራ ሁለት አገሮች ሆኑ ። ዘኁ፡ ፳፩ ፳፫ ።

በእስራኤል ልጆች አውራጃ መካከል ያሉ የሌዋውያን አገሮች ሁሉ በነዚያ አገሮች ዙርያ ካሉ ከመሠማሪያዎቻቸው ጋራ አርባ ስምንት አገሮች ናቸው ።

በአገር ያሉ ያንዷቱም ያንዷቱም አገር መሠማሪያዋ እንደነዚያ አገሮች መሠማሪያ ነው ። ዘኁ፡ ፴፭ ፯ ።

ኢያሱም በየአውራጃቸው ምድርን ከፍሎ ጨረሰ፤ እግዚአብሔርም ለእስራኤል ልጆች ላባቶቻቸው የማለላቸውን አገር ሰጥቶአቸው ወርሰዋት በውስጧ ኖሩ ።

እግዚአብሔር ላባቶቻቸው እንደ ማለላቸው በዙርያቸው ካሉ ጠላቶቻቸው አሳረፋቸው እግዚአብሔር ጠላቶቻቸውን በእጃቸው ጥሏቸዋልና ከዚያ በኋላ ከጠላቶቻቸው ሁሉ በፊታቸው ማንም ማን የተጣላቸው የለም ።

እግዚአብሔር ለእስራኤል ልጆች ከተናገራቸው በጎ ነገር ሁሉ ሁሉም ደረሳቸው እንጂ አንድም የቀረች ቃል የለችም ።

## ምዕራፍ ፳፪ ።

ከዚህ በኋላ ኢያሱ የጋድ ልጆችንና የሮቤል ልጆችን የምናሴ ነገድ እኩሌታን ጠራቸው ።

የእግዚአብሔር ወዳጁ ሙሴ ያዘዛችሁን ሁሉ እናንተ ሰምታችኋል፤ እኔ ያዘዝኋችሁንም ቃሌን ሰማችሁ ።

ብዙ በሆኑ በነዚያ ወራቶች እስከዚች ቀን ድረስ ወንድሞቻችሁን አልተዋቸሁም የፈጣሪያችን የእግዚአብሔር ትእዛዝ ጠበቃችሁ ።

አሁን ግን ፈጣሪያችን እግዚአብሔር እንደነገራቸው ወንድሞቻችሁን አሳረፋቸው ።

አሁንም ተመልሳችሁ ወደ ቤታችሁ ግቡ፤ የእግዚአብሔር አገልጋይ ሙሴ በዮርዳኖስ ማዶ ወደ ሰጣችሁ አገር አውራጃችሁ ተመለሱ ። ኢያ፡ ፲፫ ፰፣ ፳፫ ፩ ።

ነገር ግን ፈጣሪያችሁ እግዚአብሔርን ልትወዱት በሥርዓቱም ሁሉ ጸንታችሁ ልትኖሩ ትእዛዙንም ልትጠብቁ በፍጹም ሰውነታችሁና በፍጹም ልቡናችሁ ልትከተሉትና

ዕቀቡ ትእዛዘ ወትትልውዎ ወታምልክዎ በኵሉ ልብክሙ
ወበኵሉ ነፍስክሙ ።
፯ ወባረኮሙ ኢያሱ ወፈነዎሙ፣ ወአተዉ ውስተ አብ
ያቲሆሙ ።
፰ ወለመንፈቀ ነገደ ምናሴ ወሀቦሙ ሙሴ በባሳን፤ ወለ
መንፈቆሙሰ ወሀቦሙ ኢያሱ ምስለ አኀዊሆሙ በማዕዶተ
ዮርዳኖስ ዘኀበ ባሕር ።
፱ ወሰበ ፈነዎሙ ኢያሱ ውስተ አብያቲሆሙ፣ አተዉ
ምስለ ብዙኅ ንዋይ፣ ወምስለ ብዙኅ እንስሳ፣ ወምስለ ወ
ርቅ ወብሩር ወብርት ወሐፂን ወአልባስ ብዙኅ ጥቀ ዘተ
ከፈሉ በርበረ ፀሮሙ ምስለ አኀዊሆሙ ።
፲ ወተመይጡ ወአተዉ ደቂቀ ሮቤል ወደቂቀ ጋድ ወመን
ፈቀ ነገደ ምናሴ እምደቂቀ ሼል እምነ ሴሎ ዘምድረ ከነአን
ከመ ይሑሩ ውስተ ገለአድ ውስተ ደወሎሙ ወውስተ ርስ
ቶሙ ዘተዋረስዋ በትእዛዘ እግዚአብሔር በእደ ሙሴ ።
፲፩ ወበጽሑ ውስተ ገለአድ ዘዮርዳኖስ ዘምድረ ከነአን
ወነደቁ ደቂቀ ጋድ ወደቂቀ ሮቤል ወመንፈቀ ነገደ ምናሴ
በህየ ምሥዋዐ ዐቢየ ዘያስተርኢ ።
፲፪ ወሰምዑ ደቂቀ እስራኤል ከመ ነደቁ ምሥዋዐ ደቂቀ
ሮቤል ወደቂቀ ጋድ ወመንፈቀ ነገደ ምናሴ በውስተ ደወ
ለ ምድረ ከነአን በኀበ ገለአድ ዘዮርዳኖስ በማዕዶቶሙ
ለደቂቀ እስራኤል ።
፲፫ ወሰምዑ ደቂቀ እስራኤል ኵሎሙ ወተጋብኡ ውስተ
ሴሎ ከመ ይዕርጉ ወይትቃተልዎሙ ።
፲፬ ወለአኩ ደቂቀ እስራኤል ኀበ ደቂቀ ሮቤል ወኀበ ደ
ቂቀ ጋድ ወኀበ መንፈቀ ነገደ ምናሴ ውስተ ምድረ ገለ
አድ ፊንሐስሃ ወልደ አልአዛር ወልደ አሮን ካህን ።
፲፭ ወዐሠርተ መላእክተ ምስሌሁ መልአክ አሐዱ አሐዱ
እምአብያተ አበዊሆሙ እምኵሉ ነገደ እስራኤል እደወ
መላእክተ አብያተ አበዊሆሙ ወመሳፍንተ እሙንቱ ለእስ
ራኤል ።
፲፮ ወበጽሑ ኀበ ደቂቀ ጋድ ወኀበ ደቂቀ ሮቤል ወኀበ
መንፈቀ ነገደ ምናሴ ውስተ ገለአድ ።
፲፯ ወነገርዎሙ ወይቤልዎሙ ከመዝ ይቤሉ ኵሉ ተዓይኑ
እግዚአብሔር ምንትኑ ዛቲ አበሳ ዘአበስክሙ ቅድመ አም
ላከ እራኤል ከመ ትኅድጉ ዮም ተሊዎቶ ለእግዚአብሔር
ወትንድቁ ለክሙ ምሥዋዐ ወከመ ትክሐድዎ ዮም ለእግ
ዚአብሔር ።
፲፰ አስተንአስክሙኑ ኀጢአቶ ለፌጎር ዘኢነጻሕነ እምኔሃ
እስከ ዮም፣ ወኮነ መቅሠፍት ላዕለ ትዕይንቱ ለእግዚአብ
ሔር ።
፲፱ ዮምኒ አንትሙ ኀደግሙ ተሊዎቶ ለእግዚአብሔር
ወእምከመ አንትሙ ዮም ክሕድክምዎ ለእግዚአብሔር
ጌሠመ ላዕለ ኵሉ እስራኤል ይከውን መቅሠፍት ።
፳ ወይእዜኒ እመ ትንእስክሙ ደወለ ምድርክሙ ዕድዉ
ውስተ ኢየሩሳም ደወለ ምድረ እግዚአብሔር ኀበ ትነብር
ህየ ደብተራሁ ለእግዚአብሔር ወተዋረሱ ምስሌነ ወኢት
ክሐድዎ ለእግዚአብሔር እስመ ነደቅሙ ምሥዋዐ አፍአ
እምሥዋዒሁ ለእግዚአብሔር አምላክነ ።

ልታመልኩት የእግዚአብሔር ወዳጁ ሙሴ ያዘዛችሁን ሕጉ
ንና ትእዛዙን ታደርጉ ዘንድ ፈጽማችሁ ተጠበቁ አላቸው።
ኢያሱም መርቆ አሰናበታቸው፣ ወደ ቤቶቻቸውም
ገቡ ። ዘዐ፡ ፴፱ ፵፫ ። ኢያ፡ ፳፮ ፯ ።
ለምናሴ ነገድ እኩሌታም ሙሴ ባሳንን ሰጣቸው ለእ
ኩሌቶቹ ግን ኢያሱ ከወንድሞቻቸው ጋር በባሕር በኩል
ባለች በዮርዳኖስ መካከል ሰጣቸው ። ኢያ፡ ፲፯ ፭ ።
ኢያሱ ወደየ ቤታቸው በሰናበታቸው ጊዜ እጅግ ብዙ
ከሆነ ከብትና ከብዙ ገንዘብ ጋራ ከወርቅና ከብር ከብረትና
ከናስ ጋራ ተመለሱ፣ ከጠላቶቻቸውም ምርኮ ከወንድሞ
ቻቻውም ጋር የተካፈሉት ልብስ እጅግ ብዙ ነው ።
የጋድና የሮቤል ልጆች የነገደ ምናሴም እኩሌታ ከእ
ስራኤል ልጆች ተለይተው በእግዚአብሔር ትእዛዝ በሙ
ሴ ቃል ወደ ወረሷት ርስታቸውና ወደ አውራጃቸው ወደ
ገለዓድ ለመሄድ በከነዓን ካለች ከሴሎም ተመለሱ ።
የከነዓን ዕጣ በምትሆን በዮርዳኖስ ማዶ ወዳለች ወደ
ገለዓድ ደርሰው የሮቤል ልጆችና የጋድ ልጆች፣ የነገደ
ምናሴም እኩሌታ በዚያ የሚታይ ታላቅ መሠውያን ሠሩ።
የእስራኤልም ልጆች የጋድ ልጆች የሮቤል ልጆች የነ
ገደ ምናሴም እኩሌቶች በከነዓን አውራጃ ባለች በእስራ
ኤል ልጆች ማዶ የዮርዳኖስ ዕጣ በምትሆን በገለዓድ መሠ
ውያን እንደ ሠሩ ሰሙ ። ዘዳ፡ ፲፫ ፲፪፣ ፲፬ ፲፭ ።
የእስራኤል ልጆች ሁሉ ሰምተው ወጥተው ይዋጉዋ
ቸው ዘንድ በሴሎ ተሰበሰቡ ። መሳ፡ ፳ ፩ ።
የእስራኤል ልጆች ከጋድ ልጆችና ከሮቤል ልጆች ከነ
ገደ ምናሴም እኩሌታ ዘንድ አገልጋይ የሚሆን የአሮን ልጅ
የአልአዛር ልጅ ፊንሐስን ገለአድ ወደሚባል አገር ላኩ ።
ዓሥር አለቆችም ከሱ ጋራ ሄዱ፣ ከእስራኤል ልጆች
ሁሉ የተቈጠሩ ያባቶቻቸው ወገኖች አለቆች አንዱም አን
ዱም አለቃ ከአባቶቻቸው ወገን የተቈጠሩ ናቸው፣ እነ
ዚህም የእስራኤል ሹማምንት ናቸው ። ዘኍ፡ ፩ ፬ ።
በገለዓድ ወዳሉ ወደ ሮቤል ልጆች ወደ ጋድ ልጆች
ወደ ነገደ ምናሴም እኩሌቶች ደርሰው ።
የእግዚአብሔር ሠራዊት ሁሉ እንዲህ አሉ ገዥ የሚ
ሆን እግዚአብሔርን ማምለክ ትታችሁ መሠውያን ትሠሩ
ዘንድ እግዚአብሔርንም አሁን ትክዱት ዘንድ በእስራኤል
ፈጣሪ ፊት የሠራችኋት ይህች ኃጢአት ምንድር ናት፤ አሉ
ብለው ነገሯቸው ። ዘሌ፡ ፲፯ ፱ ። ዘኍ፡ ፲፱ ፱ ።
እስካሁን ድረስ ከዚ ያልነጻን ጣኦቱን በማምለክ ያገኘ
ችን ኃጢአትን በእግዚአብሔር ሠራዊት ላይ የተደረገ
ያነን መቅሠፍት ታቃልሉታላችሁን፤ ።
አሁንም እናንተ እግዚአብሔርን ማምለክ ተዋችሁ፣
አሁን እናንተ እግዚአብሔርን ከካዳችሁት ነገ በእስራኤል
ሁሉ መቅሠፍት ይደረጋል ። ዘኍ፡ ፲፮ ፳፪ ።
አሁንም ያገራችሁ አውራጃ ከነሳችሁ የእግዚአብሔር
ማደሪያ ድንኳን ወዳለችበት ወደ እግዚአብሔር አገር አው
ራጃ ወደ ኢየሩሳሌም ተሻግራችሁ ከኛ ጋራ ውረሱ፣ ከፈ
ጣሪያችን ከእግዚአብሔር መሠውያ ውጭ መሠውያን
ሠርታችኋልና እግዚአብሔርን አትክዱት ።

፳፩ አኮኑ አካን ወልደ ዛራ አመ አበሰ ወጌገየ ወነሥአ እም ዘኅሩም ላዕለ ኵሉ ትዕይንተ እስራኤል ኮነ መቅሠፍት ሰበ በሕቲቱ አበሰ ፥ በኑ በሕቲቱ ሞተ በኀጢአቱ ።

፳፪ ወአውሥኡ ደቂቀ ሮቤል ወደቂቀ ጋድ ወመንፈቀ ነገደ ምናሴ ወይቤልዎሙ ለመላእክተ እስራኤል እንዘ ይብሉ ፥ እግዚአብሔር ውእቱ አምላክ ወእግዚእ ወአምላክ አማልክት ውእቱ ።

፳፫ እግዚአብሔርሰ ውእቱ የአምር ወለእስራኤልኒ ውእቱ የአምሮ ከመ አኮ ለክሒድ ወለአብሶ ዘገበርነ ቅድሜሁ ለእግዚአብሔር ወእመ አኮሰ ኢያድኅነነ ዮም ።

፳፬ ወእመኒ ምሥዋዐ ነደቅነ ለነ ከመ ንክሐዶ ለእግዚአብሔር አምላክነ ወከመ ናዕርግ ላዕሌሁ መሥዋዕተ ወቍርባነ ወእመኒ ከመ ንግበር ላዕሌሁ መሥዋዕተ መድኃኒት ውእቱ ለሊሁ እግዚአብሔር ለይትኃሠሠ ።

፳፭ ወእመአኮሰ በበይነ ፍርሀተ ነገር ዘገበርናሁ ለዝንቱ ግብር እንዘ ንብል ከመ ኢይበልዎሙ ጌሠመ ውሉድክሙ ለውሉድነ ምንት ብክሙ ምስለ እግዚአብሔር አምላከ እስራኤል ።

፳፮ እስመ አቀመ እግዚአብሔር ወሰነ ማእከሌክሙ ወማእከሌነ ለደቂቀ ሮቤል ወለደቂቀ ጋድ ወለመንፈቀ ነገደ ምናሴ ለዮርዳኖስ አቀሞ ወአልብክሙ ክፍል ምስለ እግዚአብሔር ወይሬስይዎሙ ነኪራነ ውሉድክሙ ለውሉድነ ከመ ኢያውዕእዎሙ እምአምልኮ እግዚአብሔር ።

፳፯ ወንቤ ከመ ንግበር ከመዝ ወንንድቅ ዘንተ ምሥዋዐ አኮ በበይነ ቍርባን ወአኮ በበይነ መሥዋዕት ።

፳፰ አላ ከመ ይኩን ዝንቱ ስምዐ ማእከሌነ ወማእከሌክሙ ማእከለ ውሉድነ ወማእከለ ውሉድክሙ እምድኅሬነ ከመ ያምልክዎ አምልኮ ለእግዚአብሔር በቅድሜሁ በቍርባን ክሙ ወበመሥዋዕተ መድኃኒትክሙ ፥ ወኢይበልዎሙ ውሉድክሙ ለውሉድነ ጌሠመ አልብክሙ ክፍል ምስለ እግዚአብሔር ።

፳፱ ወንቤ አመ ኮነ ድኅረ ወይቤሉነ ጌሠመ አው ለውሉድነ ከመ ይበልዎሙ ናሁ ርእዩ አምሳለ ምሥዋዑ ለእግዚአብሔር ዘገብሩ አበዊነ አኮ በበይነ ቍርባን ወአኮ በበይነ መሥዋዕት አላ ከመ ይኩን ስምዐ ማእከሌነ ወማእከሌክሙ ።

፴ ሐሰ ለነ እስከ ነኀድግ ተሊዎቶ ለእግዚአብሔር ዮም ከመ ንክሐዶ ለእግዚአብሔር ወከመ ንንድቅ ለነ ምሥዋዐ ለቍርባን ወለመሥዋዕተ ሰላም ወለመሥዋዕተ መድኃኒት ዘእንበለ ውስተ ምሥዋዒሁ ለእግዚአብሔር አምላክነ ዘቅድመ ደብተራሁ ።

፴፩ ወሰበ ሰምዐ ፊንሐስ ካህን ወኵሎሙ መላእክተ ተዓይን ወመሳፍንተ እስራኤል እለ ምስሌሁ ቃለ ዘይቤል

የዛራ ልጅ አካን ፈጽሞ ስለ በደለ እርም ነገርንም ስለ ወሰደ በእስራኤል ሠራዊት ላይ መቅሠፍት የተደረገ አይደለምን! ብቻውን ቢበድል በኃጢአቱ ብቻውን ሞተን! አላቸው ። ኢያ፥ ፯ ፳ ።

የጋድ ልጆችና የሮቤል ልጆች የነገደ ምናሴም እኩሌቶች እግዚአብሔር ገዥም ፈጣሪም ነው ፥ የአማልክትም አምላክ ነው ብለው ለእስራኤል መልእክተኞች መለሱላቸው ።

እግዚአብሔር ግን ሁሉን ያውቃል ይህን ሥራ የሠራነው እግዚአብሔርን ለመካድና ለመበደል እንዳይደለ እስራኤልን እሱ ያውቀዋል ፤ ይህስ ካልሆነ አሁን አያድነን ።

እኛ መሠውያንውም ብንሠራ ፈጣሪያችን እግዚአብሔርን እንክደው ዘንድ ቍርባኑንና መሥዋዕቱን በመሠውያው ላይ ለመሠዋት አይደለም የድኅነት መሥዋዕትን በሱ እናደርግ ዘንድ የሠራነውስ ቢሆን እሱ እግዚአብሔር ይመራመረን ። ዘዳ፥ ፲፱ ፲፰ ። ፩ ሳሙ፥ ፳ ፲፯ ።

ነገ ልጆቻችሁ ልጆቻችንን ከእስራኤል ፈጣሪ ከእግዚአብሔር ጋራ ምን አላችሁ፤ እንዳይሉዋቸው ብለን ነገር ስለ መፍራት ይህን ሥራ የሠራነውስ ካልሆነ እግዚአብሔር ይመራመረን ። ዘፍ፥ ፴ ፴፫ ። ዘፀ፥ ፲፪ ፲፫ ።

እግዚአብሔር በኛና በናንተ መካከል ለጋድ ልጆችና ለሮቤል ልጆች ለነገደ ምናሴም እኩሌቶች ዮርዳኖስን ድንበር አድርጎ አጽንቶታልና ከእግዚአብሔር ጋር ዕድል ፈንታ የላችሁም ብለው ልጆቻችሁ ልጆቻችንን ባዕድ አድርገው እግዚአብሔርን ከማምለክ እንዳያወጡዋቸው ብለን ይህን አደረግን ።

ስለዚህም መሠውያን እንሠራ ዘንድ እንሥራ አልን እንጂ ለሚቃጠል መሥዋዕት ወይም ለሌላ መሥዋዕት አይደለም ። ኢያ፥ ፳፪ ፳፰፥ ፳፬ ፳፯ ።

ነገር ግን በኛና በናንተ መካከል ድኅነት በሚገኝበት መሥዋዕትና በቍርባናችሁ በፊቱ እግዚአብሔርን ያመልኩት ዘንድ ነገ ልጆቻችሁ ልጆቻችንን ከእግዚአብሔር ጋር ዕድል ፈንታ የላችሁም እንዳይሉዋቸው ከኛም በኋላ በልጆቻችንና በልጆቻችሁ መካከል ይህ ምስክር ይሆን ዘንድ ነው እንጂ ስለ መሥዋዕትና ስለ ቍርባን አይደለም።

ኋላ ይህ በተደረገ ጊዜ ነገ ይህ ምንድር ነው፤ ብሉን ጊዜ ወይም ልጆቻችንን እንዲህ ባሏቸው ጊዜ እነሆ አባቶቻችን የሠሩት የእግዚአብሔርን መሥዋዕት መሠውያ አምሳል እዩ ይሉዋቸው ዘንድ ብለን በናንተና በኛ መካከል ምስክር ይሆን ዘንድ ነው እንጂ፥ ስለ መሥዋዕትና ስለ ቍርባን አይደለም ። ዘዳ፥ ፬ ፲፯ ።

በደብተራ ኦሪት አንጻር ባለ በፈጣሪያችን በእግዚአብሔር መሠውያ እንሠዋለን እንጂ እግዚአብሔርን እንክደው ዘንድ የፍቅር መሥዋዕትንና ቍርባንን ድኅነት የሚገኝበት መሥዋዕትንም ልንሠዋ እኛ መሠውያን እንሠራ ዘንድ እግዚአብሔርን ማምለክ እስክንተው ድረስ ደርሰን ለኛ አገባባችን አይደለም አሏቸው ። ኢያ፥ ፳፬ ፲፯ ።

የሠራዊቱ አለቆች ሁሉና አገልጋይ የሚሆን ፊንሐስ ከሱም ጋር ያሉ የእስራኤል ሹማምንት የጋድ ልጆችና

ዎሙ ደቂቀ ሮቤል ወደቂቀ ጋድ ወመንፈቀ ነገደ ምናሴ እርመሙ ወተፈሥሑ ።

፴፩ ወይቤሎሙ ፊንሐስ ወልደ አልአዛር ካህን ለደቂቀ ሮቤል ወለደቂቀ ጋድ ወለመንፈቀ ነገደ ምናሴ ዮም አእመርነ ከመ ሀለወ እግዚአብሔር ምስሌነ እስመ ኢአበስክሙ ቅድመ እግዚአብሔር ዘንተ ኃጢአተ ወእስመ አድኃንክምዎሙ ለእስራኤል እምእዴሁ ለእግዚአብሔር ።

፴፪ ወገብአ ፊንሐስ ወልደ አልአዛር ካህን ወመላእክተ ተዓይንኒ ምስሌሁ ኀበ ደቂቀ እስራኤል ወሖሩ ምስሌሆሙ መላእክት እምደቂቀ ሮቤል ወእምደቂቀ ጋድ ወእመንፈቀ ነገደ ምናሴ እምገለአድ ውስተ ምድረ ከነአን ኀበ ደቂቀ እስራኤል ።

፴፫ ወነገርዎሙ ለደቂቀ እስራኤል ወአደሞሙ ዝንቱ ነገር ወሰበ ነገርዎሙ ለደቂቀ እስራኤል ባረክዎ ለአምላከ ደቂቀ እስራኤል ወይቤሉ ኢነዓርግ እንከ ኀቤሆሙ ከመ ንትቃተሎሙ ወከመ ናጥፍኣ ለምድረ ደቂቀ ሮቤል ወደቂቀ ጋድ ወመንፈቀ ነገደ ምናሴ ዘነበሩ ላዕሌሃ ።

፴፬ ወሰመዮ ኢያሱ ለውእቱ ምሥዋዕ ስምዕ ዘሮቤል ወዘጋድ ወዘመንፈቀ ነገደ ምናሴ ወይቤሉ እስመ ስምዕ ውእቱ ማእከሎሙ ከመ እግዚአብሔር ውእቱ አምላኮሙ ።

ምዕራፍ ፳፫ ።

፩ ወእምዝ እምድኅረ ብዙኅ መዋዕል እምድኅረ አዕረፎሙ እግዚአብሔር አምላክ እስራኤል እምኵሉ ፀሮሙ ዘዓውዶሙ ወልህቀ ኢያሱ ወኀለፈ መዋዕሊሁ ።

፪ ጸውዐ ኵሎ ደቂቀ እስራኤል ወሊቃናቲሆሙ ወመላእክቲሆሙ ወጸሐፍቶሙ ወመኳንንቲሆሙ ወይቤሎሙ ናሁ ረሳዕኩ አንሰ ወኀለፈ መዋዕልየ ።

፫ ወለሊክሙ ርኢክሙ ኵሎ ዘገብረ እግዚአብሔር አምላክነ ላዕለ አሕዛብ እለ ቅድመ ገጽክሙ ከመ እግዚአብሔር አምላክነ ፀብአሙ ለነ ።

፬ ወናሁ ርእዩ ኀደጉ ለክሙ አሕዛበ እለ ተርፉ ውስተ እድዋሊክሙ ዘዘሕዘቢክሙ ወዘእምዮርዳኖስ ኵሎ አሕዛበ ዘሠረውክዎሙ ወባሕር ዐቢይ ምዕራበ ፀሐይ ወሰንክሙ ።

፭ ወእግዚአብሔር አምላክክሙ ውእቱ ያጠፍኦሙ ለክሙ እምቅድመ ገጽክሙ ወትወርሱ ምድሮሙ በከመ ይቤለነ እግዚአብሔር አምላክነ ።

፮ ወእጽንዑ ጥቀ ከመ ትዕቀቡ ወከመ ትግበሩ ኵሎ ዘጽሑፍ ውስተ መጽሐፈ ሕጉ ለሙሴ ከመ ኢትትገኀሡ እምኔሁ እምዘእዘዘክሙ ሙሴ ኢለየማን ወኢለፀጋም ከመ ኢተአብሱ ።

፯ ወኢትባኡ ውስተ እሉ አሕዛብ እለ ተርፉ እምኔክሙ ወአስማተ አማልክቲሆሙ ኢይሰመይ በውስቴትክሙ ወኢትምሐሉ በሙ ወኢትስግዱ ሎሙ ወኢታምልክዎሙ ።

፰ አላ ለእግዚአብሔር አምላክክሙ ትልውዎ በከመ ገብረ ለክሙ እስከ ዛቲ ዕለት ።

የሮቤል ልጆች የነገደ ምናሴም እኩሌቶች የነገሩዋቸውን ቃል በሰሙ ጊዜ ደስ ብሏቸው ዝም አሉ ።

አገልጋይ የሚሆን የአልአዛር ልጅ ፊንሐስም የጋድ ልጆችንና የሮቤልን ልጆች የነገደ ምናሴንም እኩሌቶች በእግዚአብሔር ፊት ይህን ኃጢአት አልሠራችሁምና ሽኤልንም ከእግዚአብሔር እጅ አድናችኋቸዋልና እግዚአብሔር በረድኤት ከኛ ጋራ እንዳለ አሁን አወቅን አላቸው።

የአገልጋዩ አልአዛር ልጅ ፊንሐስም ከሱ ጋራ ከሉ ከሠራዊቱ አለቆችም ጋራ ወደ እስራኤል ልጆች ተመለሱ ከጋድ ልጆችና ከሮቤል ልጆች ከነገደ ምናሴም እኩሌታ የተቈጠሩት አለቆችም ከእስራኤል ልጆች ዘንድ ከገለዓድ ወደ ከነዓን ከነሳቸው ጋራ ሄዱ ። ኢያ፡ ፳፪ ፲፡ ፲፩ ፲፭ ።

ለእስራኤል ልጆች ነገሩዋቸው ይህም ነገር እስራኤልን ደስ አሰኛቸው ፤ ለእስራኤልም ልጆች በነገሩዋቸው ጊዜ የእስራኤል ልጆችን ፈጣሪ አመሰገኑት ፤ የጋድ ልጆችና የሮቤል ልጆች የነገደ ምናሴም ልጆች እኩሌቶች የሚኖሩበት አገራቸውን እናጠፋት ዘንድ እንግዲህ ወደ ነሳቸው አንወጣም አሉ ። ፩ ዜና መዋ፡ ፳፱ ፳፩ ።

ኢያሱም ያነን ግምብ የጋድና የሮቤል የነገደ ምናሴም እኩሌታ ምስክር አለው ፤ (እስራኤልም) ፈጣሪያቸው እሱ እግዚአብሔር እንደሆነ በመካከላቸውም እሱ ምስክር ነውና ምስክር አሉት ። ዘፀ፡ ፲፰ ፬ ።

ምዕራፍ ፳፫ ።

የእስራኤል ፈጣሪ እግዚአብሔር በዙርያቸው ካሉ ከጠላቶቻቸው ሁሉ ካሳረፋቸው ከብዙ ዘመን በኋላ ኢያሱም የሕፃንነቱ ወራት አልፎ ከረጀ በኋላ ።

ሽማግሎቻቸውንና የእስራኤልን ልጆች ሁሉ ጸሐፊዎቻቸውን አለቆቻቸውና መኳንንቶቻቸውንም ጠርቶ እነሆ እኔ አረጀሁ የሕፃንነቴም ወራት አለፈ ። ዘዳ፡ ፴፩ ፳፰ ።

ፈጣሪያችን እግዚአብሔር እንዳጠፋልን በፊታችሁ ባሉ አሕዛብ ፈጣሪያችን እግዚአብሔር ያደረገውን ሁሉ እናንተ አይታችኋል ። ዘፀ፡ ፲፱ ፲፬ ።

እነሆ በየወገኖቻችሁ በአውራጃችሁ የቀሩ አሕዛብን ከዮርዳኖስ ጀምሮ ያጠፋኋቸው አሕዛብን ሁሉ ለናንተ እንደተውኩላችሁ እዩ ወሰናችሁም በፀሐይ መግቢያ ያለ ሰፊ ባሕር ነው ። ኢያ፡ ፲፫ ፮ ፡ ፲፰ ፲፱ ።

ፈጣሪያችሁ እግዚአብሔር እሱ ከፊታችሁ ያጠፋላችኋል ፤ ፈጣሪያችን እግዚአብሔር እንደ ነገረን አገራቸውንም ትወርሳላችሁ ። ዘፀ፡ ፳፫ ፴ ። ኢያ፡ ፲፫ ፮ ።

ሕጉን ትጠብቁ ዘንድ የሙሴ ሥርዓቱ በተጻፈበት መጽሐፍ የተጻፈውን ሁሉ ታደርጉ ዘንድ እንዳትበድሉ ፤ ሙሴ ካዘዛችሁ ከሱ ወደ ቀኝም ወደ ግራም እንዳትሉ ፈጽማችሁ ልቡናችሁን አጽኑ ። ዘዳ፡ ፭ ፴፪ ።

ከናንተም ወደ ቀሩ ወደ አሕዛብ አትግቡ ፤ የጣኦቶቻቸውም ስም በናንተ ዘንድ አይጠራ ፤ አትማሉባቸው አትስገዱላቸውም አታምልኩዋቸውም ። ዘፀ፡ ፳፫ ፴፫ ።

እስከዚች ቀን ድረስ እንዳደረገላችሁ ፈጣሪያችሁ እግዚአብሔርን አምልኩት እንጂ እነሳቸውን አታምልኳቸው።

፱ ወውእቱ እግዚአብሔር ያጠፍኦሙ እምቅድመ ገጽክሙ ለአሕዛብ ዐበይት ወጽኑዓን ወለክሙሰ አልቦ ዘተቃወመክሙ ቅድሜክሙ እስከ ዛቲ ዕለት ።

እሱ እግዚአብሔር ብዙ ጽኑ የሚሆኑ አሕዛብን ከፊታችሁ ያጠፋቸዋል ፤ እናንተን ግን እስከዚች ቀን ድረስ ማንም በፊታችሁ የተቋቋማችሁ የለም ።

፲ አሐዱ ብእሲ እምኔክሙ ይሰድድ ዐሠርተ ምእተ እስመ እግዚአብሔር አምላክነ ይፀብእ ለክሙ በከመ ይቤለነ።

ፈጣሪያችን እግዚአብሔር እንደነገረን ይዋጋላችኋልና ከእናንተ አንድ ሰው ሺሑን ሰው ድል ያደርጋቸዋል ።

፲፩ ወተዓቀቡ ጥቀ ነፍስክሙ ከመ ታፍቅርዎ ለእግዚአብሔር አምላክነ ።

ፈጣሪያችን እግዚአብሔርን ትወዱት ዘንድ ሰውነታችሁን አጥብቃችሁ ጠብቁ ። ዘዳ፣ ፬ ፲፭ ። ኢያ፣ ፳፪ ፭ ።

፲፪ ወእመሰ ተመየጥክሙ ወኀደግምዎ ትገብኡ ውስተ እሉ አሕዛብ እለ ተርፉ ምስሌክሙ ወኢትትዋሰቡ ምስሌሆሙ ወኢትደመሩ ውስቴቶሙ ።

(እግዚአብሔርን) ትታችሁ ወደ አሕዛብ ብትመለሱ ግን ከናንተ ጋራ በቀሩ በነዚያ አሕዛብ እጅ ትጠፋላችሁ ከነሳቸውም ጋር አትጋቡ ፤ በግብርም አንድ አትሁኑ ።

፲፫ ወለሊክሙ አእምሩ ከመ ኢያጠፍኦሙ እንከ እግዚአብሔር አምላክነ ለእሉ አሕዛብ እምቅድሜክሙ ወይከውኑክሙ እንከ መሥገርተ ወዕቅፍተ ወቀኖታተ ውስተ ሰኰናዊክሙ ወይደኑጹክሙ ውስተ አዕይንቲክሙ እስከ ትጠፍኡ እምድር ቡርክት ዘወሀበክሙ እግዚአብሔር አምላክክሙ ።

(ይህን ካደረጋችሁ) ፈጣሪያችን እግዚአብሔር እነዚህን አሕዛብን እንግዲህ ከፊታችሁ እንደማያጠፋቸው እናንተ ዕወቁ ፤ እንግዲህ ዕንቅፋትና ወጥመድ በእግራችሁም ችንካር ይሆኑባችኋል ፈጣሪያችሁ እግዚአብሔር ከሰጣችሁ ከተባረከች አገር እስክትጠፉ ድረስ ዓይኖቻችሁን ይጠነቁሏችኋል ።

፲፬ ወአንሰ አሐውር ውስተ ፍኖት ከመ ኵሉ እለ ውስተ ምድር ፤ ወአእምሩ በኵሉ ልብክሙ ወበኵሉ ነፍስክሙ ከመ ኢተኀድገት ወኢ አሐቲ ቃል እምኵሉ ሠናይት ዘይቤለክሙ እግዚአብሔር አምላክነ ።

እኔም በዚህ ዓለም እንዳሉ ሰዎች ሁሉ ወደ ሞት ጐዳና እሄዳለሁ ፤ ፈጣሪያችን እግዚአብሔር ከነገራችሁ በጎ ነገር ሁሉ አንዲት ቃል ስንኳን እንዳልቀረች በፍጹም ሰውነታችሁና በፍጹም ልቡናችሁ ዕወቁ ።

፲፭ ወኵሉ በጽሐነ ወአልቦ ዘኢረከብነ እምኔሁ ፤ ወበከመ በጽሐክሙ ኵሉ ቃል ሠናይ ዘይቤለክሙ እግዚአብሔር አምላክክሙ ከማሁ ያመጽእ ላዕሌክሙ እግዚአብሔር አምላክክሙ ኵሎ ቃለ እኩየ እስከ ያጠፍአክሙ እምዛቲ ምድር ቡርክት ዘወሀበክሙ እግዚአብሔር ።

ሁሉ ደረሰን ከሱ ያላገኘነው የለም ፤ ፈጣሪያችሁ እግዚአብሔር የነገራችሁ በጎ ነገር ሁሉ እንደደረሳችሁ እግዚአብሔር ከሰጣችሁ ከዚች ከተመረቀች አገር እስኪያጠፋችሁ ድረስ ፈጣሪያችሁ እግዚአብሔር እንደዚያ በናንተ ክፉ ነገር ሁሉ ያመጣባችኋል ።

፲፮ እምከመ ኀደግሙ ኪዳኖ ለአምላክክሙ ዘወሀበክሙ ወዘአዘዘክሙ ወለመ ሖርክሙ ወአምለክሙ አማልክተ ባዕድ ወሰገድክሙ ሎሙ ይትመዓዕ በመዐት እግዚአብሔር ላዕሌክሙ ወፍጡነ ያጠፍአክሙ እምድር ዘወሀበክሙ ።

ያዘዛችሁንና የሰጣችሁን የፈጣሪያችሁ የእግዚአብሔርን መሐላ ካፈረሳችሁ ሂዳችሁ ልዩ በሆኑ ጣኦታትን ብታመልኩና ብትሰግዱላቸው እግዚአብሔር በናንተ ላይ ተቈጥቶ ከሰጣችሁ አገር ላይ ፈጥኖ ያጠፋችኋል ።

## ምዕራፍ ፳፬ ።

፩ ወአስተጋብኦሙ ኢያሱ ለኵሉ ሕዝበ እስራኤል ውስተ ሴሎም ወጸውዖሙ ለሊቃናተ እስራኤል ወለመላእክቲሆሙ ወለጸሐፍቶሙ ወአቀሞሙ ቅድመ እግዚአብሔር ።

ኢያሱ የእስራኤልን ወገኖች ሁሉ በሴሎም ሰበሰባቸው ፤ አለቆቻቸውንና የእስራኤልን ሽማግሎች ጸሐፍቶቻቸውንም ጠርቶ በእግዚአብሔር ፊት አቆማቸው ።

፪ ወይቤሎሙ ኢያሱ ለኵሉ ሕዝብ ከመዝ ይቤ እግዚአብሔር አምላከ እስራኤል ፤ በማዕዶተ ፈለግ ነበሩ አበዊክሙ ቀደምት ታራ አቡሁ ለአብርሃም ወአቡሁ ለናኮር ወአምለኩ ባዕዳነ አማልክተ ።

ኢያሱ ሕዝቡን ሁሉ የኃል ፈጣሪ እግዚአብሔር እንዲህ አለ ፤ የቀደሙ አባቶቻችሁ የናኮር አባትና የአብርሃም አባት ታራ በወንዝ ማዶ ነበሩ ፤ ልዩ ጣኦታትን አመለኩ ።

፫ ወነሣእክዎ ለአብርሃም አቡክሙ እማዕዶተ ፈለግ ወወሰድክዎ ውስተ ኵሉ ምድረ ከናአን ወአስተባዛኅኩ ዘርኦ ።

አባታችሁ አብርሃምን ከወንዝ ማዶ አምጥቼ ወደ ከነዓን ወሰድሁት ፤ ዘሩንም አበዛሁለት ።

፬ ወወሀብክዎ ይስሐቅሃ ፤ ወለይስሐቅኒ ያዕቆብሃ ወኤሳውሃ ፤ ወወሀብክዎ ለኤሳው ደብረ ሴይር ወአውረስክዎ ፤ ወያዕቆብሰ ወደቂቁ ወረዱ ውስተ ግብጽ ወኮኑ በህየ ሕዝበ ዐቢየ ወብዙኀ ወጽኑዐ ወሣቀይዎሙ ግብጽ ።

ለአብርሃም ይስሐቅን ሰጠሁት ፤ ለይስሐቅም ዔሳውንና ያዕቆብን ሰጠሁት ፤ ለዔሳው የሴይርን ተራራ ሰጥቼ አወረስኩት ፤ ያዕቆብና ልጆቹ ግን ወደ ግብጽ ወረዱ ፤ በዚያም ብዙ ወገን ሆኑ ብዙ ጽኑም የግብጽም ሰዎች መከራ አጸኑባቸው ።

፭ ወፈነውኩ ሙሴሃ ወአሮንሃ በከመ ገበርኩ በማእከሎሙ ወቀተልክዎሙ ለግብጽ በበይነ ዘገብሩ ላዕሌሆሙ ።

ሙሴንና አሮንን ላክሁ በመካከላቸው እንዳደረግሁትም በነሱ ላይ ክፉ ስላደረጉ የግብጽን ሰዎች አጠፋኋቸው ።

፮ ወእምድኅረ ዝንቱ አውፃእክዎሙ ለአበዊክሙ ወበእክሙ ውስተ ባሕር ወዴገኑክሙ ግብጽ ወተለዉክሙ ወተ

ከዚህ በኋላ አባቶቻችሁን አወጣኋቸው ወደ ባሕረ ኤርትራም ገባችሁ ፤ የግብጽም ሰዎች ፈጽመው ተከተሏ

ለዊ. ድኅሬሆሙ ለአበዊክሙ በአፍራስ ወበሠረገላት ው
ስተ ባሕረ ኤርትራ ።
፯ ወጸራሕክሙ ኀበ እግዚአብሔር ወፈነውኩ ደመና
ወቆባረ ማእከሌክሙ ወማእከለ ግብጽ ወአስተጋባእኩ ላዕ
ሌሆሙ ባሕረ ወደፈኖሙ፤ ወርእያ አዕይንቲክሙ ኵሎ
ዘገበርኩ በምድረ ግብጽ ወነበርክሙ ብዙኃ መዋዕለ ው
ስተ ገዳም ።
፰ ወወሰድኩክሙ ውስተ ምድረ አሞሬዎን እለ ይነብሩ
በማዕዶተ ዮርዳኖስ ወተቃተሉሙ ሙሴ ወአግባእክዎሙ
ውስተ እዴክሙ ወተዋረስክሙ ምድሮሙ ወአጥፋእክ
ዎሙ እምቅድሜክሙ ።
፱ ወተንሥአ ባላቅ ወልደ ሰፎር ንጉሠ ሞአብ ወተቃተ
ሎሙ ለእስራኤል ወለአከ ወጸውዖ ለበለዓም ወልደ ቤዖር
ከመ ይርግምክሙ ።
፲ ወኢፈቀድኩ አጥፍእክሙ ወበረከተ ባረኩክሙ ወአ
ድኀንኩክሙ እምእዴሁ ።
፲፩ ወዐደውክሙ ዮርዳኖስ ወበጻሕክሙ ውስተ ኢያሪኮ
ወተቃተሉክሙ እለ ይነብሩ ውስተ ኢያሪኮ ወአሞሬዎን
ወከናኔዎን ወፌርዜዎን ወኤዌዎን ወኢያቡሴዎን ወኬጤ
ዎን ወጌርጌሴዎን ወአግባእክዎሙ ውስተ እዴክሙ ።
፲፪ ወፈነውኩ ላዕሌሆሙ እምቅድሜክሙ ዐከተ ወሰደድ
ክዎሙ እምቅድሜክሙ ለዐሠርቱ ወክልኤቱ ነገሥት ዘአ
ሞሬዎን አኮ በሰይፍከ ወአኮ በቀስትከ ።
፲፫ ወወሀብኩክሙ ምድረ ዘኢጻመውክሙ ባቲ ወአህጉረ
እለ ኢነደቅክሙ ነበርክሙ ውስቴቶን ወአዕፃደ ወይን
ወዘይት ዘኢተከልክሙ ትበልዑ አንትሙ ።
፲፬ ወይእዜኒ ፍርህዎ ለእግዚአብሔር ወአምልክዎ በጽ
ድቅ ወበርትዕ ወአሰስሉ እምኔክሙ አማልክተ ነኪር ዘአ
ምለኩ አበዊክሙ በማዕዶተ ፈለግ ወበግብጽ ወአምልክ
እምልክዎ ለእግዚአብሔር ።
፲፭ ወእመሰ ኢፈቀድክሙ ታምልክዎ ለእግዚአብሔር ኅ
ረዩ ለክሙ ዮም መነ ታመልኩ እመ አኮ አማልክተ አበ
ዊክሙ እለ ማዕዶተ ፈለግ ወእመ አኮ አማልክተ አሞሬ
ዎን እለ ውስተ ምድሮሙ ሀሎክሙ ዮም ወአንሰ ወቤትየ
እግዚአብሔርሃ ናመልክ እስመ ቅዱስ ውእቱ ።
፲፮ ወአውሥኡ ኵሉ ሕዝብ ወይቤሉ ሐሰ ለነ እስከ ነኅ
ድጎ ለእግዚአብሔር ወናመልክ ባዕዳነ አማልክተ ።
፲፯ ወለነሰ እግዚአብሔር አምላክነ እስመ ውእቱ አምላክ
ወውእቱ አውፅአነ ለነ ወለአበዊነ እምግብጽ ወእምቤተ
ቅኔት ወኵሎ ዘገብረ ለነ ተአምረ ዐበይተ ወዐቀበነ በኵሉ
ፍኖት እንተ በቲ ሖርነ በውስተ ኵሉ አሕዛብ እለ ኀለፍነ
ላዕሌሆሙ ።
፲፰ ወአውፅኦሙ እግዚአብሔር ለአሞሬዎን ወለኵሉ አሕ
ዛብ እለ ይነብሩ ውስተ ምድር እምቅድሜነ ወከማሁ ንሕ
ነኒ ናመልክ ለእግዚአብሔር እስመ ውእቱ አምላክነ ።
፲፱ ወይቤሎሙ ኢያሱ ለሕዝብ ኢትክሉ አምልኮቶ ለእግ

ችሁ በፈረስና በሠረገላ ሁነው አባቶቻችሁን እስከ ኤርትራ
ባሕር ድረስ አባረሩዋቸው ። ዘፀ፣ ፲፬ ፴፯ - ፶፩ ።
እናንተ ወደ እግዚአብሔር ጮኻችሁ እኔም በግብጽ
ሰዎችና በናንተ መካከል ጽጋግንና ደመናን አመጣሁ፤ የኤ
ርትራንም ባሕር በነሳቸው ላይ ሰበሰብኩ ውኃም አሰጠ
ማቸው በግብጽ ያደረግሁትን ሁሉ ዓይኖቻችሁ አዩ፤ ከናን
ተም ጋራ በምድረ በዳ ብዙ ዘመን ኖርሁ ። ዘፀ፣ ፲፬ ፲ ።
በዮርዳኖስ ማዶ ወደሚኖሩ ወደአሞሬዎንም አገር
ወሰድኳችሁ ሙሴም ተዋጋቸው በእጃችሁም ጣልኋቸው
አገራቸውንም ወረሳችሁ በፊታችሁም አጠፋኋቸው ።
ዘኍ፣ ፳፩ ፳፩ - ፴፭ ።
የሞዓብ ንጉሥ የሰፎር ልጅ ባላቅም ተነሥቶ እስራኤ
ልን ተዋጋቸው፤ ይረግማችሁም ዘንድ የቢዖርን ልጅ በለ
ዓምን ልኮ አስጠራው ። ዘኍ፣ ፳፪ ፭ ። ዘዳ፣ ፳፫ ፬ ።
አጠፋችሁም ዘንድ አልወደድሁም ምርቃንን መረቅ
ኋችሁ፤ ከመርገሙ አዳንኋችሁ ። ዘዳ፣ ፳፫ ፳፰ ።
ዮርዳኖስን ተሻግራችሁ ወደ ኢያሪኮም ደረሳችሁ፤
በኢያሪኮ የሚኖሩ ከናኔዎንና አሞሬዎን፤ ኤዌዎንና ፌር
ዜዎን፤ ኬጤዎንና ኢያቡሴዎን፤ ጌርጌሴዎንም ተዋጓችሁ
እነዚህንም በእጃችሁ ጣልኋቸው ። ኢያ፣ ፫ ፲፩ ።
ከናንተ በፊት ተርናጣጭ ዝንብ አመጣሁባቸው ዓሥ
ራ ሁለቱንም የአሞሬዎን ነገሥታት ከፊታችሁ አስወጥቼ
ሰደድኋቸው፤ ነገር ግን ያጠፋኻቸው በጦርህና በሰይፍህ
አይደለም ። ዘፀ፣ ፳፫ ፳፰ ። ዘዳ፣ ፯ ፳ ።
ያልደከማችሁበትን አገር ሰጠኋችሁ፤ ባልሠራችኋ
ቸውም መንደሮች ኖራችሁ፤ እናንተ ያልተከላችሁትን
የዘይቱንና የወይኑን ፍሬ ትበላላችሁ ።
አሁንም እግዚአብሔርን ፍሩት፤ በሚገባና በእውነ
ትም አምልኩት አባቶቻችሁ በግብጽና በወንዝ ማዶ በሰ
ርያ አባቶቻችሁ ያመለኳቸው የአሕዛብ ጣኦታትንም ከና
ንተ አስወግዱ፤ እግዚአብሔርንም ፈጽማችሁ አምልኩት ።
እግዚአብሔርን ታመልኩት ዘንድ ባትወዱ ግን አሁን
ምረጡ፤ ማንንን ታመልኩ፤ ወይስ በወንዝ ማዶ አባቶቻ
ችሁ ያመልኳቸው የነበሩ ጣኦታትን ታመልኩን፤ ወይስ
አሁን በአገራቸው ያላችሁባቸው የአሞሬዎንን ጣኦታት
ታመልኩን፤ ወገኖቼና እኔ ግን እሱ ልዩ ነውና እግዚአብ
ሔርን እናመልከለን አላቸው ። ኢያ፣ ፳፬ ፲፬ ። ሩት ፩ ፲፮ ።
ሕዝቡም ሁሉ እግዚአብሔርን ትተን ልዩ የሆኑ ጣኦ
ታትን እናመልክ ዘንድ አገባብችን አይደለም ።
ፈጣሪ እሱ ነውና፤ ከአገዛዝ ቤት ከግብጽ አባቶቻች
ንንና እኛን አውጥቶናልና ታላላቅ ተአምራትን ሁሉ ያደ
ረገልን እሱ ነውና፤ በነሳቸው ላይ አልፈን በሄድንባቸው
አሕዛብ ሁሉ በሄድንበት ጐዳና ሁሉ ጠብቆናልና ።
ዘጸ፣ ፮ ፲፪ ።
እግዚአብሔር በምድሪቱ (በከነዓን) የሚኖሩ አሕዛብን
ሁሉና አሞሬዎንን ከፊታችን አጥፍቶልናልና ለኛስ ፈጣ
ሪያችን እሱ ነውና፤ እኛም እንደዚሁ እግዚአብሔርን እና
መልከዋለን ብለው መለሱለት ።
ኢያሱም ሕዝቡን እሱ ልዩ ነውና፤ እሱ ለአምላክነቱ

ዚአብሔር እስመ ቅዱስ ውእቱ ወአምላክ ቀናኢ ውእቱ ወኢያኅድግ ለክሙ ኃጢአቲክሙ ወአበሳክሙ ።
፳ ወእምከመ ኀደግምዎ ለእግዚአብሔር ወአምለክሙ ባዕዳነ አማልክተ የሐውር ወይሣቅየክሙ ወያጠፍአክሙ ህየንተ ዘአሠነየ ላዕሌክሙ ።
፳፩ ወይቤልዎ ሕዝብ ለኢያሱ ዳዕሙ ለእግዚአብሔር ናመልክ ።
፳፪ ወይቤሎሙ ኢያሱ ለሕዝብ ለሊክሙ ስምዕ ላዕለ ርእስክሙ ከመ ለሊክሙ ኀረይክምዎ ለእግዚአብሔር ታምልክዎ ወይቤሉ ስምዕ ንሕነ ።
፳፫ ወይቤሎሙ ይእዜኒ አሰስሉ አማልክተ ነኪር ዘማኤ ክሙ ወአርትዑ ልበክሙ ኀበ እግዚአብሔር አምላከ እስራኤል ።
፳፬ ወይቤልዎ ሕዝብ ለኢያሱ ለእግዚአብሔር አምላክነ ናመልክ ወቃለ ዚአሁ ንሰምዕ ።
፳፭ ወተከየደሙ ኢያሱ ለሕዝብ በይእቲ ዕለት ወወሀቦሙ ሕገ ወፍትሐ በሴሎም በቅድመ ደብተራሁ ለአምላከ እስራኤል ።
፳፮ ወጸሐፎ ኢያሱ ለዝንቱ ነገር ውስተ መጽሐፈ ሕጉ ለእግዚአብሔር ወነሥአ ኢያሱ እብነ ዐቢየ ወአቀማ መትሕተ ዕፀ ጠርቤንቶስ ቅድመ እግዚአብሔር ።
፳፯ ወይቤሎሙ ኢያሱ ለኵሎሙ ሕዝብ ናሁ ዛቲ እብን ስምዕ ላዕሌክሙ እስመ ይእቲ ሰምዐት ኵሉ ዘተብህለ በኀበ እግዚአብሔር ዘከመ ተናገርክሙ ዮም ፡ ወትኩንክሙ ይእቲ ስምዐ ላዕሌክሙ በደኃሪ መዋዕል ለእመ ሐሰውክምዎ ለእግዚአብሔር አምላኪየ ።
፳፰ ወፈነዎሙ ኢያሱ ለሕዝብ ወአተዉ ኵሎሙ ውስተ በሐውርቲሆሙ ወአምለክዎ እስራኤል ለእግዚአብሔር በኵሉ መዋዕሊሁ ለኢያሱ ወበኵሉ መዋዕሊሆሙ ለሊቃናት እለ አኀዉ መዋዕሊሆሙ እምድኅረ ኢያሱ ወኵሎሙ እለ ርእዩ ግብሮ ለእግዚአብሔር ኵሎ ዘገብረ ለእስራኤል ።
፳፱ ወኮነ እምድኅረ ዝንቱ ሞተ ኢያሱ ወልደ ነዌ ገብረ እግዚአብሔር ወምእት ወዐሠርቱ ዓመታቲሁ ።
፴ ወቀበርዎ ውስተ ደወለ ርስቱ ተምናሥራኅ ውስተ ደብረ ኤፍሬም እመንገለ መስዕ ለደብረ ገዓስ ህየ ።
፴፩ ወወደዩ ምስሌሁ ውስተ መቃብሩ ኀበ ቀበርዎ መጣብሐ ዘእዝኅ እለ ቦቱ ገዘሮሙ ለደቂቀ እስራኤል በገልገላ እመ ወፅኡ እምግብጽ በከመ አዘዘ እግዚአብሔር ፡ ወሀየ ሀለዋ እስከ ዮም ።
፴፪ ወአዕፅምቲሁ ለዮሴፍ ዘአውፅኡ እምግብጽ ወከረዩ ውስተ ሰቂማ ውስተ አሐዱ ኀብር ዘገራህት ዘተሣየጣ ያዕቆብ እምአሞሬዎን እለ ይነብሩ ውስተ ሰቂማ በምእት አባግዕ ወወሀበ ለዮሴፍ ክፍሎ ።
፴፫ ወኮነ እምድኅረ ዝንቱ አልአዛር ወልደ አሮን ሊቀ ክህናት ሰበ ሞተ ወቀበርዎ ውስተ ምድረ ብአር ዘውሀበ ለፊንሐስ ወልዱ በደብረ ኤፍሬም ።
፴፬ ወይእተ አሚረ ነሥኡ ደቂቀ እስራኤል ታቦቶ ለእግዚአብሔር ወወሰድዋ ምስሌሆሙ ወፊንሐስ ኮነ ሊቀ ክህ

የሚቀና ፈጣሪ ነውና ፡ አምልኮቶቹን ከለቀናችሁት በደላችሁንና ኃጢአታችሁን ይቅር አይላችሁም ። ዘሌ፡ ፲፱ ፪።

እግዚአብሔርንም ትታችሁ ሌላ ጣኦታትን ካመለካችሁ ከናንተ ተለይቶ ሂዶ መከራ ያጸናባችኋል በጎ ነገር ስላደረገላችሁ ፈንታ ያጠፋችኋል አላቸው ።
ሕዝቡም ኢያሱን እግዚአብሔርን ብቻ እናመልከዋለን አሉት ። ኢሱ፡ ፩ ፳፰ ። ኤር፡ ፲፮ ፲፫ ።
ኢያሱም ሕዝቡን ታመልኩት ዘንድ እናንተ እግዚአብሔርን እንደመረጣችሁት እናንተ ለራሳችሁ ምስክር ናችሁ አላቸው ፡ እነሱም አዎን ምስክር ነን አሉት ።
አሁንም በናንተ ዘንድ ያሉ የአሕዛብ ጣኦታትን አስወግዳችሁ ልቡናችሁን ወደ እስራኤል ፈጣሪ አቅኑ አላቸው። ዘፍ፡ ፴፭ ፪። ኢያ፡ ፲ ፲፩ ።
ሕዝቡም ኢያሱን ፈጣሪያችን እግዚአብሔርን እናመልከዋለን የሱንም ቃል እንሰማለን አሉት።
ኢያሱም በዚያች ቀን ሕዝቡን ተማማላቸው በእስራኤል ፈጣሪ ድንኳንም ፊት በሴሎም ፍርድንና ሥርዓትን አስተማራቸው ። ዘፀ፡ ፲፭ ፳፭ ። ፪ ነገ፡ ፲፩ ፲፯ ።
ኢያሱ ይህንን ነገር የእግዚአብሔር ሕግ በተጻፈበት በኦሪት ጻፈው ፡ ታላቅ ደንጊያም አምጥቶ በእግዚአብሔር ፊት በጉዋም ሥር አቆማት ። ዘዳ፡ ፴፩ ፳፬ ።
ኢያሱ ሕዝቡን ሁሉ አሁን እንደ ተናገራችሁ በእግዚአብሔር ዘንድ የተነገረውን ሰምታለችና እነሆ ይህች ደንጊያ በናንተ ምስክር ናትና ኋላ በፍጻሜ ዘመን ፈጣሪ እግዚአብሔርን ብትክዱት ይህች (ደንጊያ) በናንተ ምስክር ትሁንባችሁ አላቸው ። ዘፍ፡ ፴፩ ፩። ዘሌ፡ ፲፱ ፲፩ ።
ኢያሱም ሕዝቡን አሰናበታቸው ሁሉም ወዳገራቸው ገቡ ፡ እስራኤልም በኢያሱ ዘመን ሁሉ ከኢያሱም ዘመን በኋላ ዘመናቸው በበዛ በሽማግሎችም ዘመን ሁሉ ለእስራኤል ያደረገውን የእግዚአብሔር ተአምራቱን ሁሉ በዩ ሰዎች ሁሉ ዘመን እግዚአብሔርን አመለኩት ።
ከዚህ በኋላ እንዲህ ሆነ ፡ የእግዚአብሔር አገልጋይ የነዌ ልጅ ኢያሱ ሞተ ዘመኑም መቶ ዓሥር ነበረ ።
ከገዓስ ተራራ በስተቀኝ የኤፍሬም ዕፃ በምትሆን በርስቱ ተምናሥራሕ አውራጃ ቀበሩት ።
ከግብጽ በወጡ ጊዜ እግዚአብሔር እንዳዘዘው የእስራኤልን ልጆች በገልገላ የገረዘባቸው የቡልጭት ምላጮችን እሱን በቀበሩበት መቃብር ከሱ ጋራ አብረው ቀበሩ እስከሁን ድረስም በዚያ አሉ ። ዘዳ፡ ፴፩ ፪ ።
ከግብጽም ያወጡት የዮሴፍን አጥንት ያዕቆብ በሰቂማ ከሚኖሩ ከአሞሬዎን በመቶ በጎች በገዛት ለዮሴፍ ፈንታ አድርጎ በሰጣት እርሻ በአንድ ወገኑ በሰቂማ ቈፍረው ቀበሩት ። ዘፍ፡ ፶፭ ፳፭ ፡ ፴፫ ፲፱ ።
ከዚህ በኋላ እንዲህ ሆነ ፡ የአሮን ልጅ የካህናቱ አለቃ አልአዛር በሞተ ጊዜ ለልጁ ለፊንሐስ በሰጠው በአር በምትባል አገር በኤፍሬም ዕጣ ቀበሩት ።
የዚያን ጊዜ የእስራኤል ልጆች የእግዚአብሔር ማደሪያ ታቦትን ከነሱ ጋራ ይዘዋት ሄዱ ፡ ፊንሐስም በሳቡቱ

ናት ሀገንተ አልአዛር አቡሁ እስከ አመ ሞተ ወክረዩ ሎቱ ውስተ ገባእን ውስተ ምድሮሙ፡ ወአተዉ ኵሎሙ ደቂቀ እስራኤል ውስተ አብያቲሆሙ ወውስተ አህጉሪሆሙ።

፴፩ ወአምለኩ ደቂቀ እስራኤል አስጠራጢን ወአስጣሮት ወአማልክተ አሕዛብ እለ ዐውዶሙ ወአግብኦሙ እግዚአብሔር ውስተ እደ ኤግሎም ንጉሠ ሞአብ፡ ወቀነዮሙ ዐሠርተ ወሰመንተ ዓመተ።

ስለ አልአዛር ፈንታ እስኪሞት ድረስ ሊቀ ክህነት ሆነ፡ በገባዖን ባለች በአገራቸው መቃብር ቈፈሩለት፡ የእስራኤል ልጆች ሁሉ ወደ አገሮቻቸውና ወደ ቤቶቻቸው ገቡ።

ከዚህ በኋላ የእስራኤል ልጆች አስጣሮትንና አስጠራጢንን በዙርያቸው ያሉ የአሕዛብን ጣዖታት አመለኩ፡ እግዚአብሔርም በሞዓብ ንጉሥ በኤግሎም እጅ ጣላቸው ዓሥራ ስምንት ዓመት ገዛቸው።

ተፈጸመ ኦሪት ዘኢያሱ፡
ወስብሐት ለእግዚአብሔር ዘኢይቀብል ብሕረ ተውዳሱ፡
አሜን።

ለእግዚአብሔር ለዘለዓለሙ ክብር ምስጋና ይግባውና
ሆሼዕ (ኢያሱ) የተናገረው መጽሐፍ መላ
ተፈጸመ፡ አሜን በእውነት።

# ኦሪት ዘመሳፍንት

## ምዕራፍ ፩።

፩ ወኮነ እምድኅረ ሞተ ኢያሱ ተስእሉ ደቂቀ እስራኤል
ኀበ እግዚአብሔር እንዘ ይብሉ መኑ የዐርግ ለነ ኀበ ከና
ኔዎን መልእክ ዘይትቃተሎሙ ለነ።
፪ ወይቤሎሙ እግዚአብሔር ይሁዳ ይዕርግ ወናሁ አግ
ባእክዋ ለምድር ውስተ እዴሁ።
፫ ወይቤሎ ይሁዳ ለስምዖን እኁሁ ዕርግ ምስሌየ በው
ስተ መክፈልትየ ወንትቃተሎሙ ለከነአን ወእሐውር አነኒ
ምስሌከ በውስተ መክፈልትከ ወሖረ ስምዖን ምስሌሁ።
፬ ወዐርገ ይሁዳ ወአግብአሙ እግዚአብሔር ለከናኔዎን
ወለፌርዜዎን ውስተ እዴሁ ወቀተሎሙ በባዜቅ እልፈ
ብእሴ።
፭ ወረከብዎ ለአዶንቤዜቅ በባዜቅ ወተቃተልዎ ወቀተ
ልዎሙ ለከናኔዎን ወለፌርዜዎን።
፮ ወጐየ አዶንቤዜቅ ወዴገንዎ ወተለውዎ ወአኀዝዎ
ወመተሩ አርእስተ እደዊሁ ወእገሪሁ።
፯ ወይቤሎሙ አዶንቤዜቅ ዘሰብዓ ነገሥት አርእስተ እደ
ዊሆሙ ወእገሪሆሙ ምቱራት ሀለዉ አስተጋቢእየ በታ
ሕተ ማእድየ ወበከመ ገበርኩ ከማሁ ፈደየኒ እግዚአብ
ሔር ወወሰድዎ ኢየሩሳሌም ወሞተ በህየ።

፰ ወተቃተሉ ደቂቀ ይሁዳ ምስለ ኢየሩሳሌም ወአስተ
ጋብእዋ ወቀተልዋ በአፈ ሐፂን ወአውዐዩ ሀገራ በእሳት።

፱ ወእምዝ ወረዱ ደቂቀ ይሁዳ ይትቃተልዎሙ ለከናኔ
ዎን እለ ይነብሩ ውስተ አድባር።
፲ ወሖረ ይሁዳ ውስተ ከናኔዎን እለ ይነብሩ ውስተ ኬብ
ሮን ወወፅኡ ሰብአ ኬብሮን ወተቀበልዎሙ ወስማ ለኬብ
ሮን ትካት ቀርያርበቃሲፌር ወቀተልዎሙ ለሴሲ ወለአኪ
ማም ወለታሚን ትውልደ ኤናቅ።

፲፩ ወሖሩ እምህየ ኀበ እለ ይነብሩ ዳቤር፤ ወስማ ለዳቤር
ትካት ሀገረ መጽሐፍ።
፲፪ ወይቤ ካሌብ ለዘቀተላ ለሀገረ መጽሐፍ ወአስተጋብኣ
እሁቦ አስካሃ ወለትየ ትኩኖ ብእሲተ።
፲፫ ወአስተጋብኣ ጎቶንያል ወልደ ቄኔዝ እኁሁ ለካሌብ
ዘይንእስ ወወሀቦ አስካሃ ወለቶ ትኩኖ ብእሲተ።
፲፬ ወሶበ ለሐዊር አምከራ ጎቶንያል ትስእሎ ለአቡሃ ይጸ

## ምዕራፍ ፩።

ኢያሱ ከሞተ በኋላ እንዲህ ሆነ፤ ወደ ከናኔዎን ወጥቶ የሚዋጋልን አለቃ ማነው፤ ብለው የእስራኤል ልጆች ወደ እግዚአብሔር ጠየቁ። ዘኍ፡ ፳፮ ፳፩።

እግዚአብሔርም ይሁዳ ይዝመት፤ እነሆ ከነዓንን በ እጁ አግብቸለታለሁ አላቸው። መሳ፡ ፳ ፲፰።

ይሁዳም ወንድሙ ስምዖን በኔ ዕጣ ከኔ ጋራ ውጣ፤ (ዝመት) የከነዓንን ሰዎች እንዋጋቸው፤ እኔም በንተ ዕጣ ከንተ ጋራ እሄዳለሁ አለው፤ ስምዖንም ከሱ ጋራ ሄደ።

ይሁዳም ዘመተ እግዚአብሔርም ፌርዜዎንንና ከናኔ ዎንን በእጁ ጣላቸው፤ በባዜቅም አጠፋቸው፤ እነዚህም አልፍ (ዓሥር ሺሕ) ሰዎች ናቸው። ፩ ሳሙ፡ ፲፩ ፰።

አዶንቤዜቅም አግኝተው ተዋጉት፤ ፌርዜዎንንና ከና ኔዎንንም አጠፉዋቸው።

አዶንቤዜቅም ሸሸ አሳድደውም ያዙት፤ የእጆቹንና የእግሮቹንም ጣቶች ቈረጡ።

አዶንቤዜቅ የእግሮቻቸውንና የእጆቻቸውን ጣቶች የተቈረጡ ሰባ ነገሥታት ሰብስቤ ጕልበት ገበታዬን ስመ ግባቸው ነበር፤ እኔም እንዳደረግሁ እግዚአብሔር እንደ ዚያው መለሰልኝ (ከፈለኝ) አላቸው፤ ወደ ኢየሩሳሌምም ወሰዱት፤ በዚያም ሞተ። መሳ፡ ፩ ፯። ሩት ፪ ፯።

የይሁዳም ልጆች ከኢየሩሳሌም ሰዎች ጋራ ተዋጉ፤ በጦር ወግተውም እጅ አደረጓት፤ አገሯንም በእሳት አቃጠሉ። ኢያ፡ ፲፭ ፷፫።

ከዚህም በኋላ የይሁዳ ልጆች በተራራዎች የሚኖሩት ከናኔዎንን ይዋጉዋቸው ዘንድ ወረዱ። ኢያ፡ ፱ ፩።

ይሁዳም በኬብሮን ወደ ሚኖሩ ወደ ከናኔዎን ሄደ፤ የኬብሮንም ሰዎች መጥተው ተቀበሉዋቸው (ገጠሙዋቸው) ጥንትም የኬብሮን ስሟ ቀርያር በቃሴፌር ይባል ነበር፤ የኤናቅንም ልጆች ኡኪማምንና ሴሲን ታሚንን አጠፉዋቸው። ኢያ፡ ፲ ፵፮፤ ፲፩ ፳፩።

ከዚያም በዳቤር ወደ ሚኖሩ ሰዎች ሄዱ፤ የዳቤርም ጥንተ ስሟ የወግ የታሪክ አገር ይባል ነበር።

ካሌብም የወግ የታሪክ አገርን ወግቶ እጅ ላደረጋት ሰው ሚስት ልትሆነው ልጄ አስካን እሰጠዋለሁ አለ።

የካሌብ ታናሽ ወንድሙ የቄኔዝ ልጅ ጎቶንያልም ወግ ቶ እጅ አደረጋት ሚስትም ልትሆነው ልጁ አስካን ሰጠው።

ለመሄድም በተነሣ ጊዜ ጎቶንያል መሠማሪያ በታን

ግዋ ዓፀደ ወፍር፤ ወአንጕርጕረት በዲበ አድግ ወጸርሐት ወትቤ ውስተ ብሔረ አዝያብ ፈነውከኒ፤ ወይቤላ ካሌብ ምንተ ከንኪ ።

፲፭ ወትቤሎ አስክ ሀበኒ በረከተ እስመ ብሔረ አዝያብ ፈነውከኒ ወሀበኒ ቤዛ ማይ፤ ወወሀበ ካሌብ በከመ ትፈቱ በልበ ቤዛ ሕሙም ወቤዛ ትኩዝ ።

፲፮ ወደቂቀ ዮበብ ቄንያዊ ሐሙሁ ለሙሴ ዐርጉ እምሀገረ ፊንቆን ኀበ ደቂቀ ይሁዳ ውስተ ሐቅለ ይሁዳ ዘመንገለ አዜብ ውስተ ሙራደ አራድ ወሖረ ወነበረ ምስሌሆሙ ።

፲፯ ወሖረ ይሁዳ ምስለ ስምዖን እኁሁ ወቀተልዎሙ ለከናኔዎን እለ ይነብሩ ውስተ ሴፍር ወአሕረምዎ ወአጥፍእዎ ።

፲፰ ወኢተዋረሰ ይሁዳ ለጋዛን ወለደወላ ለአስቃሎና ወለደወላ ለአቃሮን ወለደወላ ለአዛጦን ወለደወላ ወሙፋራቲሃ ።

፲፱ ወሀለወ እግዚአብሔር ምስለ ይሁዳ ወተዋረሰ ደብረ ወስእነ ተዋርሶቶሙ ለእለ ይነብሩ ውስተ ቈላት እስመ ሠረገላተ ሐፂን በሙ ።

፳ ወወሀብዎ ለካሌብ ኬብሮን በከመ ይቤ ሙሴ ወተዋረሰ እምህየ ሠለሰ አህጉረ ወአሰሰሎሙ እምህየ ለሠለስቱ ደቂቀ ኤናቅ ።

፳፩ ወለኢያቡሴዎን እለ ይነብሩ ውስተ ኢየሩሳሌም ኢያሰሰልዎሙ ደቂቀ ብንያሚ ወነበሩ ኢያቡሴዎን ምስለ ደቂቀ ብንያሚ እስከ ዛቲ ዕለት ።

፳፪ ወዐርጉ ደቂቀ ዮሴፍ እሙንቱኒ ውስተ ቤቴል ወእግዚአብሔር ምስሌሆሙ ወተዐየኑ ወርእይዋ ለቤቴል ወስማ ለይእቲ ሀገር ትካት ሎዛ ።

፳፫ ወርእዩ ሰብአ ማዕቅብ ብእሴ እንዘ ይወፅእ እምሀገር ወአኀዝዎ ወይቤልዎ አርእየነ ምብዋአ ለሀገር ወንገብር ምሕረተ ምስሌከ ።

፳፬ ወአርአዮሙ እንተ ኀበ ይበውእዋ ለሀገር ወቀተልዋ ለይእቲ ሀገር በአፈ ሐፂን ወለዝክቱሰ ብእሲ ወለአዝማዲሁ አግዐዝዎሙ ።

፳፭ ወአተወ ውእቱ ብእሲ ውስተ ምድረ ኬጤኤን ወነደቀ በህየ ሀገረ ወሰመየ ስማ ሎዛ ወውእቱ ከነ ስማ እስከ ዮም ።

፳፮ ወኢተዋረሰ ምናሴ ቤተሶን እንተ ሀገረ ሰቂቶን ወአዋልዲሃ ወኢጺአታቲሃ ወኢቀጸአድ ወአዋልዲሃ ወኢ እለ ይነብሩ ውስተ አዶር ወአዋልዲሃ ወኢ እለ ይነብሩ ውስተ በለዓም ወአዋልዲሃ ወኢ እለ ይነብሩ ውስተ መጌዶ ወአዋልዲሃ ወኢ እለ ይነብሩ ውስተ ዮበለዓም ወአዋልዲሃ ወአኀዙ ከነአን ይንበሩ ውስተ ይእቲ ምድር ።

፳፯ ወእምዝ ሶበ ጸንዑ እስራኤል መጸብሒ ረሰይዎሙ ለከነአን ወአጥፍአሰ ኢያጥፍእዎሙ ።

፳፰ ወኤፍሬምኒ ኢያጥፍእዎሙ ለከናኔዎን እለ ይነብሩ ውስተ ጋዜር ወነበሩ ከናኔዎን ማእከሎሙ ውስተ ጋዜር

እንዲሰጣት አባቷን ትለምነው ዘንድ መከራት፤ በበቅሎዋም ላይ ሁና አንጕራጕረች፤ ወደ በረኻ አገር ሰደድከኝ ብላ ጮኸች፤ ካሌብም ምን ሆንሽ፤ አላት ።

እስከም ወደ በረኻ ሰደኸኸኛልና በረከትን (ጕልት)፤ ስጠኝ ውኃ የሚጣቴንም ዋጋ ስጠኝ አለችው፤ ካሌብም በልቧ እንደ ~~ተመኘችው የታችኛውንና የመካከለኛውን ውኃ ሰጣት።~~

የሙሴ አማት የቄንያው ሰው የዮባብ ልጆችም ፊንቆን ከሚባል አገር በአራድ መውረጃ ግራ አንጻር ወዳለች ወደ ይሁዳ ዕጣ ከይሁዳ ልጆች ዘንድ ወጡ፤ እሱም ሄዶ ከወገኖቹ ጋራ ተቀመጠ ። መሳ፡ ፬ ፲፩ - ፲፯ ።

ይሁዳም ከወንድሙ ከስምዖን ጋር ሄደ፤ በሴፍር የሚኖሩ ከናኔዎንን አጠፋቸው አገሪቱንም ሕርም ብለው አጠፉዋት ። መሳ፡ ፩ ፫ ። ፪ ዜና መ፡ ፲፬ ፲ ።

ይሁዳም ጋዛን ከአውራጃዋ ጋር አስቃሎናን ከአውራጃዋ ጋር አቃሮንን ከአውራጃ ጋራ አዛጦንን ከአውራጃዋና ከመሠማሪያዎቿ ጋር አልወረሳትም ።

እግዚአብሔር (በረድኤት) ከይሁዳ ጋራ ኖረ፤ ደጋውንም ወረሰ፤ የብረት ሠረገላዎች ነበሯቸውና በቈላ የሚኖሩ ሰዎች ግን መውረስ አልተቻለውም ።

ለካሌብም ሙሴ እንዳዘዘ ኬብሮንን ሰጡት፤ ከዚያም ሠላሳ አገሮችን ወረሰ፤ ከዚያም ሦስቱን የኤናቅ ልጆችን አጠፋቸው ። ዘኁ፡ ፲፬ ፳፬ ። ዘዳ፡ ፩ ፴፮ ።

በኢየሩሳሌም የሚኖሩ ኢያቡሴዎንን ግን የብንያም ልጆች አላጠፉዋቸውም፤ ኢያቡሴዎንም እስከዚች ቀን ድረስ ከብንያም ልጆች ጋራ ኖሩ ።

እነዚያም የዮሴፍ ልጆች ወደ ቤቴል ወጡ፤ እግዚአብሔርም (በረድኤት) ከነሱ ጋር ነበረ፤ ተከማችተውም ቤቴልን አዩዋት የዚያችም አገር ጥንት ስሟ ሎዛ ይባል ነበር ። ዘኁ፡ ፲፪ ፯ ። መሳ፡ ፲፰ ፯ ።

አምባን የሚጠብቁ ሰዎች አንድ ሰው ከከተማው ሲወጣ አይተው ይዘው የከተማይቱን መግቢያ አሳየን ላንተ (ምሕረት) ወረታን እናደርግልሃለን አሉት ።

ከተማይቱን የሚገቡበትንም አሳያቸው፤ ያችንም አገር በጦር አጠፉዋት፤ ያንን ሰውና ዘመዶቹን ግን ነፃ አወጡዋቸው ።

ያም ሰው ወደ ኬጤኤን አገር ገብቶ በዚያች ከተማ ሠራ፤ ስሟንም ሎዛ አላት፤ ስሟም እስከሁን ድረስ ሎዛ ተባለ ። ኢያ፡ ፩ ፱ ። ፩ ነገ፡ ፰ ፮ ።

ምናሴም በሰቂቶን አገር ያለች ቤተሶንን ከጥቃቅን አገሮችዋ ጋራ ኢቀጸአድንም ከጥቃቅን አገሮቿ ጋር በአዶር የሚኖሩትንም ከጥቃቅን አገሮቿ ጋራ፤ በበለዓም የሚኖሩትንም ከጥቃቅን መንደሮቿ ጋራ፤ በመጌዶ የሚኖሩትንም ከጥቃቅን አገሮቿ ጋራ፤ በዮበለዓም የሚኖሩትንም ከጥቃቅን መንደሮቿ ጋራ አልወረሰም፤ የከነዓንም ሰዎች በዚያች አገር ይኖሩ ጀመር ። ኢያ፡ ፲፯ ፲፩ ፲፫ ።

ከዚያ በኋላ እስራኤል በጸኑ ጊዜ የከነዓንን ሰዎች ገባር አደረጉዋቸው፤ ማጥፋትን ግን አላጠፏቸውም ።

የኤፍሬምም ነገድ በጋዜር የሚኖሩ ከናኔዎንን አላጠፉዋቸውም፤ ከናኔዎንም በጋዜር በመካከላቸው ኖሩ፤ ገባር

ወኮንዎሙ መጸብሐ ።
፴ ወዛብሎንሂ ኢያጥፍእዎሙ ለእለ ይነብሩ ውስተ ቄድ
ሮን ወለእለ ይነብሩ ውስተ ኤማን ወነበሩ ከናኔዎን ማእከ
ሎሙ ወኮንዎሙ መጸብሐ ።
፴፩ ወአሴርኒ ኢያጥፍእዎሙ ለእለ ይነብሩ ውስተ አከ
ወኮንዎሙ መጸብሐ ወለእለ ይነብሩ ውስተ ዶር ወለእለ
ይነብሩ ውስተ ዶላፍ ወእለ ይነብሩ ውስተ ሲዶና ወእለ
ይነብሩ ውስተ አስኮድ ወኬድያ ወአፈቅ ወሮአብ ።

፴፪ ወነበረ አሴር ማእከለ ከናኔዎን እለ ይነብሩ ውስተ ይ
እቲ ምድር እስመ ስእኑ አጥፍኦቶሙ ።
፴፫ ወንፍታሌምሂ ኢያጥፍእዎሙ ለእለ ይነብሩ ውስተ
ቤተ ሳሚስ እስመ ስእኑ አጥፍኦቶሙ ወኢ እለ ይነብሩ
ውስተ ቤቴኔስ ወነበሩ ማእከሎሙ ከናኔዎን ለእለ ሀለዉ
ውስተ ይእቲ ምድር ወኮንዎሙ መጸብሐ እለ ይነብሩ
ውስተ ቤተ ሳሚስ ወውስተ ቤቴኔስ ።
፴፬ ወአጠቅዎሙ አሞሬዎን ለደቂቀ ዳን በውስተ አድባር
እስመ ኢያበውሕዎሙ ይረዱ ውስተ ቄላት ።

፴፭ ወአኀዙ አሞሬዎን ይንበሩ ውስተ ደብረ መርስኖኖስ
ዘበ ውስቴቱ ድብ ወቈናጽል ወጸንዐት እዴሆሙ ለቤተ
ዮሴፍ ላዕለ አሞሬዎን ወኮንዎሙ መጸብሐ ።
፴፮ ወደብረ አሞሬዎን ወኢዶሜዎን ላዕላይ ዘአቅራቢን
እለ ውስተ ላዕለ ኰኵሕ ።

ምዕራፍ ፪ ።

፩ ወዐርገ መልአከ እግዚአብሔር እምገልገላ ላዕለ ቀለው
ትሞኖስ ወላዕለ ቤቴል ወላዕለ ቤተ እስራኤል ወይቤሎሙ
እግዚአብሔር ይቤ አውፃእኩክሙ እምግብጽ ወአበእኩ
ክሙ ውስተ ምድር ዘመሐልኩ ለአበዊክሙ ከመ እሀብክ
ሙ ወእቤለክሙ ኢየኀድግ ኪዳንየ ዘምስሌክሙ ለዓለም ።
፪ ወአንትሙኒ ኢትትከየዱ ኪዳነ ምስለ እለ ይነብሩ
ውስተ ዛቲ ምድር ወኢ ለአማልክቲሆሙ ወኢትስግዱ
ሎሙ ወኢ ለግልፎሆሙኒ ቀጥቅጡ ወምሥዋዒሆሙኒ
ንሥቱ ወኢሰማዕክሙኒ ቃልየ እመ ገበርክሙ ዘንተ ።
፫ ወአንሂ እቤ ኢይደግም አሰስሎቶሙ ለአሕዛብ እለ እቤ
ከመ አውፅኦሙ እምቅድሜክሙ ወይከውኑክሙ ለኀዘን
ወአማልክቲሆሙኒ ይከውኑክሙ ለዕቅፍት ።

፬ ወእምዝ ሶበ ይቤሎሙ መልአከ እግዚአብሔር ለኵሉ
እስራኤል ዘንተ ነገረ ጸርሐ ኵሉ ሕዝብ ወበከየ ።

፭ ወበእንተ ዝንቱ ተሰምየ ስሙ ለውእቱ መካን መካነ
ብካይ፣ ወሦዑ በሀየ ለእግዚአብሔር ።
፮ ወፈነዎሙ ለሕዝብ ወአተዉ ደቂቀ እስራኤል ኵሎ
ሙ ውስተ አብያቲሆሙ ወውስተ ርስቶሙ ከመ ይትዋረ
ስዋ ለምድር ።
፯ ወተቀንዩ ሕዝብ ለእግዚአብሔር በኵሉ መዋዕሊሁ
ለኢያሱ ወበኵሉ መዋዕሊሆሙ ለሊቃናት ወኵሉ እለ

ንም ሆኑዋቸው ። ኢያ፣ ፲ ፴፫፣ ፲፮ ፲ ።
የዛብሎንም ነገድ በኤማን የሚኖሩትንና በቄድሮን
የሚኖሩትን ሰዎች አላጠፉዋቸውም፣ ከናኔዎንም በመካከ
ላቸው ኖሩ፣ ገባርንም ሆኑዋቸው ።
ነገደ አሴርም በአክ የሚኖሩትን ሰዎች አላጠፉዋቸ
ውም፣ ገባርንም ሆኑዋቸው፣ በዶላፍ የሚኖሩ ሰዎችንና
በዶር የሚኖሩትን ሰዎች፣ በአስኮድ የሚኖሩትንና በሲ
ዶና፣ በአፈቅና በኬድያ የሚኖሩትን በሮአብም የሚኖሩ
ትን ሰዎችን አላጠፉዋቸውም ። ኢያ፣ ፲፱ ፲፭ - ፴፭ ።
አሴርም እነሳቸውን ማጥፋት ተሰኖታልና በዚያች
አገር በሚኖሩ በከናኔዎን መካከል ኖረ ። ኢያ፣ ፲፱ ፴፰ ።
የንፍታሌም ነገድ እነሳቸውን ማጥፋት ተሰኖአቸዋ
ልና በቤተ ሳሚስ የሚኖሩትን ሰዎች አላጠፉዋቸውም፣
በቤቴኔስ የሚኖሩትን ሰዎች አላጠፉዋቸውም፣ ከናኔዎ
ንም በዚያች አገር በሚኖሩት ሰዎች መካከል ኖሩ፣ በቤ
ቴኔስና በቤተሳሚስ የሚኖሩ ሰዎች ገባር ሆኑዋቸው ።
አሞሬዎንም ወደ ቈላ ይወርዱ ዘንድ አላሰናበቱዋቸ
ውምና በደጋ የሚያስጨንቋቸው የዳንን ልጆች በቈላ አስ
ጨነቋቸው ። ኢያ፣ ፲፱ ፵ ። መሳ፣ ፲፰ ፩ ።
አሞሬዎንም ቀበሮችና ድብ በሉበት በመርስኖኖስ
ተራራ ይኖሩ ጀመር፣ የዮሴፍም ነገድ ሥልጣን በአሞሬ
ዎን ላይ ጸናች፣ ገባርንም ሆኑዋቸው ።
በዋሻ የሚኖሩ የአቅራቢን ዕጣ የሚሆኑ በላይኛው
ኤዶሜዎንና በአሞሬዎን የሚኖሩ ሰዎች ገባር ሆኑዋቸው ።

ምዕራፍ ፪ ።

ከእግዚአብሔር የተላከ መልአክ ከገልገላ ወደ ቤቴ
ልና ወደ ቀለውትሞኖስ ወደ እስራኤልም ወጥቶ መጥቶ
እግዚአብሔር ከግብጽ አውጥቼ እስጣችሁ ዘንድ ለአበቶ
ቻችሁ ወደ ማልኩላቸው አገር መሐላዬንም ለዘለዓለሙ
አላፈርስባችሁም አልኋችሁ ። ዘዳ፣ ፴፩ ፲፮ ።
እናንተም በዚች አገር ከሚኖሩ ሰዎች ጋራ መሐላን
አትማማሉ ለጣኦቶቻቸውም አትስገዱላቸው፣ ጣኦቶቻቸ
ውን ስበሩ፣ መሠውያቸውንም አፍርሱ አልኋችሁ፣ ነገር
ግን ቃሌን አልሰማችሁኝም፣ ይህንን ብታደርጉ ።
እኔም ከፊታችሁ አወጣቸው ዘንድ አወጣቸዋለሁ
ያልኳቸው አሕዛብን ዳግመኛ አላጠፋቸውም፣ ለኀዘንም
ይሆኑዋችኋል፣ ጣኦቶቻቸውም መሰናከል ይሆኑባችኋል
አልሁ አለ አላቸው ። ዘኍ፣ ፴፫ ፶፭ ። ኢያ፣ ፳፫ ፲፫ ።
ከዚህ በኋላ እግዚአብሔር የላከው መልአክ ይህንን
ነገር ለእስራኤል ሁሉ በነገራቸው ጊዜ ሕዝቡ ሁሉ ጮኸ
አለቀሰ ።
ስለዚህም ነገር የዚያ ቦታ ስሙ የልቅሶ ቦታ ተባለ፣
በዚያም ለእግዚአብሔር መሥዋዕትን ሠዉ ።
ሕዝቡንም አሰናበቱዋቸው፣ የእስራኤል ልጆች ሁሉ
ወደ ቤቶቻቸው ምድራቱንም (ከነዓንን) ይወርሷት ዘንድ
ወደ ርስታቸው ገቡ ። መሳ፣ ፪ ፱ ።
ሕዝቡም በኢያሱ ዘመን ሁሉ በአለቆችም ዘመን ሁሉ
ለእግዚአብሔር ተገዙ፣ ለእስራኤል ያደረገው የእግዚአብ

ኖኀ መዋዕሊሆሙ እምድኅረ ኢያሱ ኵሎሙ ዘአእመሩ
ኵሎ ግብረ እግዚአብሔር ዐቢየ ዘገብረ ለእስራኤል ።
፰ ወሞተ ኢያሱ ወልደ ነዌ ገብረ እግዚአብሔር እንዘ
ወልደ ምእት ወዓሥርቱ ዓመት ።
፱ ወቀበርዎ ውስተ ደብረ ርስቱ ውስተ ተምናሥራሕ
ውስተ ደብረ ኤፍሬም እምንገለ መስዑ ለደብረ ገዓስ ።
፲ ወኵላ ይእቲ ትውልድ አተዉ ኀበ አበዊሆሙ ወተን
ሥአት ካልእት ትውልድ እምድሬሆሙ ኵሉ እለ ኢየአ
ምርዎ ለእግዚአብሔር ወግብረ ዘገብረ ለእስራኤል ።

፲፩ ወገብሩ ደቂቀ እስራኤል እኪተ ቅድመ እግዚአብሔር
ወአምለኩ በዓሊምሃ ።
፲፪ ወኀደግዎ ለእግዚአብሔር አምላከ አበዊሆሙ ዘአው
ፅአሙ እምድረ ግብጽ ወተለዉ በዕዳነ አማልክተ አሕዛብ
እለ ዐውዶሙ ወሰገዱ ሎሙ ወአምዕዕዎ ለእግዚአብሔር ።
፲፫ ወኀደግዎ ለእግዚአብሔር ወአምለክዎሙ ለበዓሊም
ወለአስጠራጢን ።
፲፬ ወተምዐ እግዚአብሔር መዐተ ላዕለ እስራኤል ወአግ
ብአሙ ውስተ እደ እለ ይዔውውዎሙ ወዔወውዎሙ ወአ
እተውዎሙ ውስተ ምድረ ፀሮሙ እለ ዓውዶሙ ወኢክ
ሀሉ ተቃውሞ ቅድመ ፀሮሙ በኵሉ ዘበርበርዎሙ ።

፲፭ ወእደ እግዚአብሔር ላዕሌሆሙ በእኪት በከመ ይቤ
እግዚአብሔር ወበከመ መሐለ እግዚአብሔር ወሣቀዮሙ
ጥቀ ።
፲፮ ወአቀመ እግዚአብሔር መሳፍንተ ወአድኀኖሙ እም
እደ እለ ዔወውዎሙ ።
፲፯ ወለመሳፍንቲሆሙኒ ኢሰምዕዎሙ እስመ ዘመዉ ወተ
ለዉ አማልክተ ባዕድ ወሰገዱ ሎሙ ወአምዕዕዎ ለእግዚ
አብሔር ወኀደግዋ ፍጡነ ለፍኖት እንተ ባቲ ሖሩ አበዊ
ሆሙ ከመ ኢይስምዑ ቃለ እግዚአብሔር ወኢገብሩ
ከማሁ ።
፲፰ ወሶበ አቀመ ሎሙ እግዚአብሔር መሳፍንተ ወሀለወ
እግዚአብሔር ምስለ ውእቱ መስፍን ወአድኀኖሙ እም
እደ ፀሮሙ በኵሉ መዋዕሊሁ ለውእቱ መስፍን እስመ
ተሣሀሎሙ እግዚአብሔር እምሕማሞሙ በቅድመ እለ
ይትቃተልዎሙ ።
፲፱ ወእምዝ ሶበ ሞተ ውእቱ መስፍን ይገብኡ ካዕበ ወይ
ኤብሱ ፈድፋደ እምአበዊሆሙ ወየሐውሩ ወይተልዉ ድ
ኅረ አማልክተ ባዕድ ወያመልክዎሙ ወይሰግዱ ሎሙ
ወኢየኀድጉ እከዮሙ ወኢይገብኡ እምፍኖቶሙ እኪት።

፳ ወተምዐ እግዚአብሔር መዐተ ላዕለ እስራኤል ወይቤ
እስመ ኀደጉ እሉ ሕዝብየ ኪዳንየ ዘአዘዝክዎሙ ለአበዊ
ሆሙ ወኢሰምዑ ቃልየ ።
፳፩ ወአነኒ ኢይደግም እንከ አሰስሎ ብእሴ እምኔሆሙ
ወእምቅድሜሆሙ እምነ አሕዛብ እለ አትረፈ ኢያሱ ።
፳፪ ወኀደጎሙ ከመ ያመክሮሙ በሙ ለእስራኤል እመ
የዐቅቡ ፍኖተ እግዚአብሔር ወየሐውሩ ባቲ በከመ ዐቀቡ

ሔርን ብዙ ተአምራት ሁሉ ያወቁ ፣ ከኢያሱ በኋላ ዘመና
ቸው የበዛ ሰዎችም ሁሉ ተገዙ ። ኢያ፣ ፳ ፬ - ፴፩ ።
የእግዚአብሔር አገልጋይ የነዌ ልጅ ኢያሱም መቶ
ዓሥር ሲሆነው ሞተ ።
በገዓስ ተራራ ቀኝ አንጻር በነገደ ኤፍሬም ዕጣ ባለች
ርስቱ በምትሆን በተምናሥራሕ ቀበሩት ።
እነዚያም ወገኖች ሁሉ ሙተው አባቶቻቸው ወደ
ተቀበሩበት መቃብር ገቡ ፣ (ተቀበሩ) ከነሳቸውም በኋላ
እግዚአብሔርን የማያውቁት ለእስራኤል ያደረገውንም
ተአምራት የማያውቁ ሌሎች ትውልድ ተነሡ ።
የእስራኤልም ልጆች በእግዚአብሔር ፊት ክፉ ሥራ
ሠሩ ፣ በዓሊም የተባለ ጣኦትንም አመለኩ ።
ከግብጽ ያወጣቸው የአባቶቻቸው ፈጣሪ እግዚአብ
ሔርን ትተው በዙርያቸው ያሉ ልዩ የሆኑ የአሕዛብን ጣኦ
ታት አምልከው ሰገዱላቸው ፣ እግዚአብሔርንም አሳዘኑት።
እግዚአብሔርንም ትተው አስጠራጢንንና በዓሊምን
አመለኩዋቸው መሳ፣ ፪ ፲፩ ። መዝ፣ ፻፮ ፴፮ ።
እግዚአብሔርም በእስራኤል ቍጣን ተቈጥቶ በሚማ
ርኩዋቸው ሰዎች እጅ ጣላቸው ፣ እነሱም ማርከው ወስ
ደው በዙርያቸው ወዳሉ ጠላቶቻቸው አገር አገቡዋቸው
ማርከው በወሰዷቸው ጠላቶቻቸውም ሁሉ ፊት መከራከ
ርን አልቻሉም ። መሳ፣ ፪ ፩ ። መዝ፣ ፻፮ ፵ ።
የእግዚአብሔርም ሥልጣን እግዚአብሔር ምሎ እን
ደተናገረ በነሳቸው ላይ በመዓት አለች ፣ ፈጽሞም መከ
ራን አጸናባቸው ። ዘሌ፣ ፳፮ ፩ ። ዘዳ፣ ፳፰ ፩ ።
እግዚአብሔርም መሳፍንትን አስነሥቶ ከማረኩዋ
ቸው ሰዎች እጅ አዳናቸው ። መሳ፣ ፫ ፱ - ፲፭ ።
ለስነዋልና ልዩ የሆኑ ጣኦታትንም አምልከው ሰግደ
ዉላቸዋልና ሹማምንቶቻቸውንም አልሰሙዋቸውም እግ
ዚአብሔርንም አሳዘኑት የእግዚአብሔርን ቃል እንዳይ
ሰሙ አባቶቻቸው ጸንተው የኖሩበትንም ሥርዓት ፈጥ
ነው ተዉዋት ፣ እንደሱም አላደረጉ ። ዘፀ፣ ፴፬ ፲፭ ።
እግዚአብሔር መሳፍንትን በስነሣላቸው ጊዜ እግዚአ
ብሔር ከዚያ መስፍን ጋራ በረድኤት ኖረ ፣ በሚዋጉዋቸ
ውም ሰዎች ፊት እግዚአብሔር ከመከራቸው ይቅር ብሎ
አቸዋልና ፣ በዚያ መስፍን ዘመን ሁሉ ከጠላቶቻቸው እጅ
አዳናቸው ። ዘፍ፣ ፮ ፮ ። ዘዳ፣ ፴፪ ፴፮ ።
ከዚህ በኋላ ያ ሹም በሞተ ጊዜ ዳግመኛ ወደ ኃጢ
አት ይመለሱ ነበር ፣ ከአባቶቻቸው ይልቅ ይበድሉ ነበር ፣
ሂደውም ልዩ የሆኑ ጣኦታትን ተከትለው ያመልኳቸው
ነበር ፣ ይሰግዱላቸውም ነበር ፣ ክፋታቸውን አይተዉም
ነበር ፣ ከክፉ ሥራቸውም አይመለሱም ነበር ።
እግዚአብሔርም በእስራኤል ተቈጣ ፣ እነዚህ ወገኖቼ
ለአባቶቻቸው ያዘዝኳቸውን ቃል ኪዳኔን አፍርሰዋልና ፣
ቃሌንም አልሰሙምና ። ዘዳ፣ ፲፯ ፪ ። መሳ፣ ፪ ፲፬ ።
እኔም እንግዲህ ወዲህ ከነሳቸው ሰውን አላጠፋም ፣
ከፊታቸውም ኢያሱ ያስቀራቸው አሕዛብን አላጠፋም አለ።
የእግዚአብሔርን ሕግ ይጠብቁ እንደሆነ አባቶቻቸው
እንደ ጠበቁ በዚም ጸንተው አይኖሩም እንደሆነ እስራኤ

አበዊሆሙ ወእመ አልቦ ።
፳፫ ወኀደጎሙ እግዚአብሔር ለእሉ አሕዛብ ወኢያሰሰሎሙ ፍጡነ ወኢያግብኦሙ ውስተ እዴሁ ለኢያሱ ።

ምዕራፍ ፫ ።

፩ ወኀደጎሙ እግዚአብሔር ለእሉ አሕዛብ ከመ ያመክሮሙ በሙ ለእስራኤል ወኵሎሙ እለ ኢየአምሩ ኵሎ ፀብኦሙ ለከነአን ።
፪ ዳዕሙ በእንተ ትውልዶሙ ለደቂቀ እስራኤል ከመ ይምሀርዎሙ ቀትለ ።
፫ ወበሕቱ እለ እምቅድሜሆሙኒ ኢያእመርዎሙ ፣ ለእሉ ኃምስቱ አሕዛበ ኢሎፍሊ ወበኵሉ ከነአን ወሲዶና ወኤዊዎን እለ ይነብሩ ውስተ ሊባኖስ እምደብረ በላሄርሞን እስከ ሙበአ ኤማት ።

፬ ወተርፉ ከመ ያመክሮሙ በሙ ለእስራኤል ከመ ያእምር እመ ይሰምዑ ትእዛዘ እግዚአብሔር ዘአዘዞሙ ለአበዊሆሙ በእደ ሙሴ ።
፭ ወነበሩ ደቂቀ እስራኤል ማእከለ ከናኔዎን ወኬጤዎን ወአሞሬዎን ወፌርዜዎን ወኤዊዎን ወኢያቡሴዎን ።

፮ ወነሥኡ አዋልዲሆሙ ወአውሰቡ ወአዋልዲሆሙኒ ወሀቡ ለደቂቆሙ ወአምለኩ አማልክቲሆሙ ።

፯ ወገብሩ ደቂቀ እስራኤል እኩየ ቅድመ እግዚአብሔር ወረስዕዎ ለእግዚአብሔር አምላኮሙ ወአምለክዎሙ ለበዓሊም ወለአስጣሮት ።
፰ ወተምዐ እግዚአብሔር መዓተ ላዕለ እስራኤል ወአግብኦሙ ውስተ እደ ኵስአርስቴም ንጉሠ ሶርያ ዘመስጴጦምያ አፍላግ ወተቀንዩ ደቂቀ እስራኤል ለኵስአርስቴም ሰመንተ ዓመተ ።
፱ ወገዐሩ ደቂቀ እስራኤል ኀበ እግዚአብሔር ወአቀመሎሙ እግዚአብሔር መድኃኒተ ለእስራኤል ወአድኀኖሙ ጎቶንያል ወልደ ቄኔዝ እኁሁ ለካሌብ ዘይንእስ እምኔሁ ወተአዘዙ ሎቱ ።
፲ ወኮነ ላዕሌሁ መንፈሰ እግዚአብሔር ወኰነኖሙ ለደቂቀ እስራኤል ወወፅአ ፀብአ ወአግብአ እግዚአብሔር ውስተ እዴሁ ለኵስአርስቴም ንጉሠ ሶርያ ወአዕረፈት ምድር ኃምስተ ዓመተ ።
፲፩ ወሞተ ጎቶንያል ወልደ ቄኔዝ ፣ ወደገሙ ደቂቀ እስራኤል ገቢረ እከዩ ቅድመ እግዚአብሔር ።
፲፪ ወአጽንዖ እግዚአብሔሩ ለኤግሎም ንጉሠ ሞአብ ላዕለ እስራኤል እስመ ገብሩ እኪተ ቅድመ እግዚአብሔር ።
፲፫ ወአስተጋብአ ላዕሌሆሙ ኵሎ ደቂቀ አሞን ወአማሌቅ ወሖረ ወቀተሎሙ ለእስራኤል ወተዋረሳ ለሀገረ ፌንቆን ።
፲፬ ወተቀንዩ ደቂቀ እስራኤል ለኤግሎም ንጉሠ ሞአብ ዐሠርተ ወሰመንተ ዓመተ ።
፲፭ ወገዐሩ ደቂቀ እስራኤል ኀበ እግዚአብሔር ወአቀመሎሙ እግዚአብሔር መድኀኒተ ለእስራኤል ናኦድሃ ወልደ

ልን ይፈትንባቸው ዘንድ ተዋቸው ። ዘፀ፣ ፲፭ ፳፭ ።
እግዚአብሔር እነዚያን አሕዛብ ተዋቸው ፈጥኖም አላጠፋቸውም በኢያሱም እጅ አልጣላቸውም ።

ምዕራፍ ፫ ።

እግዚአብሔር እነዚህን አሕዛብ የተዋቸው እስራኤልን ሊፈትንባቸው ነው ፣ ሁሉም የከነዓን ሰዎች ጦርነት ሁሉ የማያውቁ ናቸው ።
ሰልፍንም ያስተምሩዋቸው ዘንድ ስለ እስራኤል ልጆች ነው እንጂ ።
ነገር ግን ከነሳቸውም አስቀድመው የነበሩ አባቶቻቸው እነዚህን አምስቱን የኢሎፍሊ ወገኖች በማጥፋት አላወቋቸውም ፣ እነዚህም በከነዓን ሁሉ በሲዶናም በኤዊዎንም ከበላሄርሞን ተራራ ጀምሮ እስከ ኤማት መግቢያ ድረስ በደጋ የሚኖሩ ናቸው ።
እግዚአብሔር በሙሴ ቃል አባቶቻቸውን ያዘዛቸውን ትእዛዝ ይሰሙ እንደሆነ ያውቅ ዘንድ እስራኤልን ሊፈትንባቸው ቀሩ ። መሳ፣ ፪ ፳፩ - ፳፪፣ ኢያ፣ ፲፫ ፪ - ፮ ።
የእስራኤልም ልጆች በኬጤዎንና በከናኔዎን ፣ በፌርዜዎንና በአሞሬዎን ፣ በኢያቡሴዎንና በኤዊዎን መካከል ኖሩ ። ዘፀ፣ ፲፫ ፭ ። መዝ፣ ፻፮ ፴፭ ።
ሴቶች ልጆቻቸውን ወስደው አጋቡ ፣ ሴቶች ልጆቻቸውንም ለወንዶች ልጆቻቸው ሰጡ ፣ ጣኦቶቻቸውንም አመለኩ ። ዘፀ፣ ፴፬ ፲፮ ።
የእስራኤልም ልጆች በእግዚአብሔር ፊት ክፉ ሥራን ሠሩ ፣ ፈጣሪያቸው እግዚአብሔርንም ዘነጉት ፣ አስጣሮትንና በዓሊምንም አመለኩዋቸው ። ዘፀ፣ ፴፬ ፲፫ ።
እግዚአብሔርም በእስራኤል ተቈጥቶ በመስጴጦምያ ወንዞች መካከል ባለች በሶርያው ንጉሥ በኵስአርስቴም እጅ ጣላቸው ፣ የእስራኤልም ልጆች ለኵስአርስቴም ስምንት ዓመት ተገዙ ። መሳ፣ ፪ ፲፬ ።
የእስራኤልም ልጆች ወደ እግዚአብሔር ጮኹ ፣ እግዚአብሔርም ለእስራኤል የሚያድናቸው መስፍንን አስነሣላቸው ፣ ከሱ የሚያንስ የካሌብ ታናሽ ወንድሙ የቄኔዝ ልጅ ጎቶንያልም አዳናቸው ፣ ለሱም ታዘዙለት ።
የእግዚአብሔርም ረድኤት አደረበት ፣ የእስራኤልንም ልጆች ገዛቸው ፣ ወደ ሰልፍ ወጣ ፣ እግዚአብሔርም የሶርያው ንጉሥ ኵስአርስቴምን በእጁ ጣለው ፣ ምድርም አምስት ዓመት አረፈች ።
የቄኔዝም ልጅ ጎቶንያልም ሞተ ፣ የእስራኤልም ልጆች ዳግመኛ በእግዚአብሔር ፊት ክፉ ሥራን ሠሩ ።
በእግዚአብሔርም ፊት ክፉ ሥራ ስለ ሠሩ እግዚአብሔር የሞዓብ ንጉሥ ኤግሎምን በእስራኤል ላይ አጸናው ።
የአማሌቅንና የአሞንን ልጆች ሰብስቦ ሄዶ እስራኤልን ወጋቸው ፣ ፌንቆንንም ወረሳት ።
የእስራኤልም ልጆች ለሞዓብ ንጉሥ ለኤግሎም ዓሥራ ስምንት ዓመት ተገዙ ። መሳ፣ ፳፰ ፵፰ ።
የእስራኤል ልጆች ወደ እግዚአብሔር ጮኹ ፣ እግዚአብሔርም ለእስራኤል የሚያድናቸው ሁለት እጆቹ ቀኝ

ጌራ ወልዶ ኢያሚን ብእሴ ዘክልኤሆን እደዊሁ የማን
ወፈነወ ደቂቀ እስራኤል አምኃ ምስሌሁ ለኤግሎም ን
ጉሠ ሞአብ ።
፲፮ ወገብረ ሎቱ ናኦድ መጥበሕተ እንተ ክልኤ አፉሃ ወእ
ንተ ስዝር ኑኃ ወቀነታ ታሕተ ቀናቱ ውስተ ሐቌሁ መን
ገለ የማኑ ።
፲፯ ወአብአ ሎቱ አምኃሁ ለኤግሎም ንጉሠ ሞአብ ወኤ
ግሎምሰ ቈጢጥ ብእሲሁ ውእቱ ጥቀ ።
፲፰ ወእምዝ ሶበ ፈጸመ ናኦድ አብአ ሎቱ አምኃሁ ፈነ
ዎሙ ለእለ ፆሩ አምኃሁ ።
፲፱ ወገብአ ኤግሎም እምቤተ አማልክት ምስለ ገልገል
ወይቤሎ ናኦድ ብየ ኅቡእ ነገር ኀቤከ ንጉሥ እንተ በሕ
ቲትከ፤ ወአዘዘ ኤግሎም ይፃእ ኵሉ እምኀቤሁ ወወፅኡ
ኵሎሙ እለ ይቀውሙ ኀቤሁ ።
፳ ወቦአ ናኦድ ኀቤሁ ወይነብር ውእቱ በሕቲቱ ውስተ
ጽርሑ ወሐጋይ ውእቱ ወይቤሎ ናኦድ ብየ ነገር ዘእነግ
ረከ ንጉሥ፤ ወተንሥአ ኤግሎም እመንበሩ ወቀርበ ።
፳፩ ወሶበ ተንሥአ አልዐለ ናኦድ እዴሁ እንተ ፀጋም
ወመልሐ መጥበሕቶ እምገቦሁ ዘየማን ወረገዞ ውስተ ከር
ሡ ለኤግሎም ።
፳፪ ወአብአ እስከ ለዐታ ወበርበሮ እስከ ዘባኑ ወመልሐ
መጥበሕቶ እምከርሡ ።
፳፫ ወወፅአ ናኦድ ጸናፌ ወዐጸወ ኆኅተ ጽርሕ ላዕሌሁ
ወቀተረ ።
፳፬ ወወፂአ ውእቱ ቦኡ ደቁ ወርእዩ ወረከቡ ኆኅተ ጽር
ሕ ዕፁወ ወይቤሉ ዮጊ ባሕቲቱ ይነብር ጽምወ ውስተ
ምግኃሠ ጽርሑ ቅስፌ ።
፳፭ ወጸንሑ እስመ ኀፍሩ ወአልቦ ዘአርኀወ ኆኀተ ጽርሕ
ወነሥኡ መርኆ ወአርኀዉ ወረከብዎ ለእግዚኦሙ ውዱቀ
ውስተ ምድር ምዉተ ።
፳፮ ወናኦድሰ አምሠጠ እስከ እሙንቱ ይትሀወኩ ወአልቦ
ዘአእመሮ ወውእቱሰ ኀለፈ እምአማልክቲሆሙ ወአም
ሠጠ ውስተ ሴይሮታ ።
፳፯ ወእምዝ ሶበ በጽሐ ውስተ ምድረ እስራኤል ነፍሐ
ቀርነ በውስተ ደብረ ኤፍሬም፤ ወወረዱ ምስሌሁ እምደ
ብር ደቂቀ እስራኤል ወውእቱ ቀድሚሆሙ ።
፳፰ ወይቤሎሙ ረዱ ትልዉኒ እስመ አግብኦሙ እግዚአ
ብሔር ለፀርነ ሞአብ ውስተ እዴነ ወወረዱ ወተለውዎ ወበ
ጽሑ ማዕዶተ ዮርዳኖስ ወአኀዙ ምዕዳወ ዮርዳኖስ ዘሞ
አብ ወኢያብሑ ሰብአ ይዕዱ ።

፳፱ ወቀተልዎሙ ለሞአብ በእማንቱ መዋዕል ወየአክሉ
እልፈ ብእሲ ኵሎሙ መስተቃትላነ ወኵሎ እደወ ኀይ
ሎሙ ወአልቦ ዘአምሠጠ እምኔሆሙ ወኢ አሐዱ ብእሲ ።

፴ ወገብኡ ሞአብ በእማንቱ መዋዕል ውስተ እዴሆሙ
ለእስራኤል ወአዕረፈት ምድር ሰማንያ ዓመተ ወኰነኖሙ
ናኦድ እስከ ሞተ ።

የሆኑ የኢያሚን ልጅ የጌራን ልጅ ናኦድን አስነሣላቸው
የእስራኤልም ልጆች ለሞዓብ ንጉሥ ለኤግሎም ከሱ ጋራ
እጅ መንሻን ላኩ ። መሳ፣ ፫ ፬፣ ፭ ፲፮ ።
ናኦድም አፍዋ ሁለት፣ ቁመቷ ስንዝር የሆነ ሰይፍን
አሠርቶ በቀኙ በኩል ባለ ወገቡ ከዝናሩ በታች ታጠቃት።

ለሞዓብ ንጉሥ ለኤግሎም እጅ መንሻውን አገባለት
ኤግሎም ግን ፈጽሞ ቀጭን ሰው ነበር ።
ከዚህ በኋላ ናኦድ ለሱ እጅ መንሻን አግብቶ በፈጸመ
ጊዜ እጅ መንሻውን የተሸከሙትን ሰዎች አሰናበታቸው ።
ኤግሎምም ከጣኦታቱ ቤት ከገልገል ጋራ ተመለሰ፤
ናኦድም ለብቻህ ባንተ ዘንድ የተሠወረ ምሥጢር አለኝ
አለ፤ ኤግሎምም ከሱ ዘንድ ሰው ይመለስ ብሎ አዘዘ፤
በሱ ዘንድ የቆሙ ሰዎችም ሁሉ ወጡ ።
ናኦድም ወደሱ ገባ፤ እሱም በእልፍኙ ብቻውን ተቀ
ምጦ ነበር ወራቱም በጋ ነበር፤ ናኦድ ንጉሥ የምነግርህ
ነገር አለኝ አለው፤ ኤግሎምም ከዙፋኑ ተነሥቶ ቀረበ ።
በተነሣም ጊዜ ናኦድ ግራ እጁን ከፍ ከፍ አድርጎ፤
ከቀኝ ጐኑ ሰይፉን መዝዞ ኤግሎምን ሆዱን ወጋው ።

እስከ ውላጋዋም ድረስ አገባበት፤ እስከ ጀርባውም
ድረስ አሜሰለው (በረበረው) ከሆዱም ሰይፉን ስቦ አወጣ።
ናኦድ ደጃፉን የኋሊት ዘግቶ ወደ አዳራሹ በር ወጣ።

እሱም በወጣ ጊዜ አሽከሮቹ ገብተው የእልፍኙ ደጃ
ፍ ተዘግቶ አገኙት፤ ወደ እዳሪ በደረገው እልፍኝ ዓይነ
ምድር ተቀምጦ ይሆናል አሉ ። ፩ ሳሙ፣ ፳፬ ፫ ።
አፍረዋልና ጠበቁ የእልፍኙን ደጃፍ የከፈተ የለም፤
መክፈቻውንም አምጥተው ደጃፉን በከፈቱ ጊዜ ጌታቸ
ውን በምድር ላይ ወድቆሙቶ አገኙት ።
ናኦድ ግን እነሳቸው እስኢታወኩ ድረስ ፈጥኖ አመ
ለጠ፤ ያወቀውም የለም፤ እሱ ግን ከጣኦቶቻቸው አልፎ
ወደ ሴይሮታ ሄዶ አመለጠ ። ዘፍ፣ ፲፱ ፲፯ ።
ከዚህ በኋላ ወደ እስራኤል አገር በደረሰ ጊዜ በኤፍ
ሬም ነገድ ዕጣ ነጋሪት መታ፤ የእስራኤልም ልጆች ከሱ
ጋር ከተራራ ወረዱ፤ እሱም በፊት በፊታቸው ይሄድ ነበር።
እግዚአብሔር የሞዓብ ሰዎች ጠላቶቻችንን በእጃችን
ጥሎልናልና ተከተሉኝ ውረዱ አላቸው፤ ተከተለዉ
ትም ወርደው ከዮርዳኖስ ማዶ ደረሱ፤ የሞዓብ ክፍል
የምትሆን የዮርዳኖስ መሻገሪያን ያዙ (ያዙ)፤ ይሻገር ዘንድ
ሰውን አላሰናበቱም ። መሳ፣ ፲፬ ፯፣ ፯ ፳፬ ።
በነዚያም ወራቶች የሞዓብን ሰዎች አጠፉዋቸው፤
እነዚያም እልፍ ሰዎችን ይሆናሉ፤ ሁሉም አርበኞች ናቸ
ው፤ የሠራዊቶቻቸውንም አለቆች ሁሉ አጠፉ፤ ከነሳቸ
ውም አንድ ሰው ስንኳ አላመለጠም ።
በዚያም ወራቶች የሞዓብ ሰዎች በእስራኤል እጅ
ወደቁ፤ ምድርም ሰማንያ ዓመት ዓረፈች፤ ናኦድም እስ
ኪሞት ድረስ ገዛቸው ። መሳ፣ ፫ ፲፩ ።

| | | |
|---|---|---|
| ወእምድኅሬዝ ቆመ ሲሜጌር ወልደ ሐናት ወቀተለ እምኢሎፍሊ ስድስተ ምእተ ብእሴ በማሕረሰ ላሕም ወውእቱኒ አድኀኖሙ ለእስራኤል ። | ፴፩ | ከዚህ በኋላ የሐናት ልጅ ሲሜጌር ተነሥቶ ከኢሎፍላውያን ስድስት መቶ ሰዎችን ገደለ፥ እሱም እስራኤልን አዳናቸው ። ዘሌ፡ ፳፮ ፲ ። መሳ፡ ፭ ፯ ። |
| **ምዕራፍ ፬ ።** | | **ምዕራፍ ፬ ።** |
| ወደገሙ ደቂቀ እስራኤል ገቢረ እኩይ ቅድመ እግዚአብሔር፥ ወናአድሰ ሞተ ። | ፩ | የእስራኤል ልጆች ዳግመኛ በእግዚአብሔር ፊት ክፉ ሥራን ሠሩ፥ ናአድ ግን ሞተ ። መሳ፡ ፪ ፲፱ ። |
| ወአግብኦሙ እግዚአብሔር ውስተ እደ ኢያሚን ንጉሠ ከናኔዎን ዘነግሠ በሶርያ ወመልአከ ሠራዊቱ ሲሳራ ወውእቱሰ ይነብር ውስተ አሴሮት ዘአሕዛብ ። | ፪ | እግዚአብሔርም በሶርያ በነገሠ በከናኔዎን ንጉሥ በኢያሚን እጅ ጣላቸው፤ ቢትወደዱም ሲሳራ ነበር፥ እሱም የአሕዛብ ዕጣ በምትሆን በአሴሮት ይኖር ነበር ። |
| ወግዕሩ ደቂቀ እስራኤል ኀበ እግዚአብሔር እስመ በተሰዐቱ ምእት ሠረገላት ዘሐፂን ወውእቱ አሕመሞሙ ለእስራኤል እንዘ ይሣቅዮሙ ዕሥራ ዓመተ ። | ፫ | ዘጠኝ መቶ የብረት ሠረገላዎች ነበረውና የእስራኤል ልጆች ወደ እግዚአብሔር ጮኹ፥ እስራኤልንም እሱ ሃያ ዓመት ያህል መከራ አጽንቶ አሳዝኖአቸው ነበር ። |
| ወዲቦራ ብእሲት ነቢይት ብእሲቱ ለፊዶት ይእቲ ትኬንኖሙ ለእስራኤል በእማንቱ መዋዕል ። | ፬ | ነቢይት የምትሆን የፊዶት ሚስት ዲቦራ በነዚያ ወራቶች እስራኤልን ትገዛቸው ነበር ። |
| ወዲቦራሰ ትነብር ኀበ ፊንቂ ማእከለ ኢያማ ወማእከለ ቤቴል ውስተ ደብረ ኤፍሬም ወዐርጉ ኀቤሃ ደቂቀ እስራኤል ከመ ይትኳነኑ ። | ፭ | ዲቦራ ግን በኤፍሬም ዕጣ ባሉ በቤቴልና በኢያማ መከከል በፊንቂ ትኖር ነበር፥ የእስራኤልም ልጆች ይፈራረዱ ዘንድ ወደሷ ወጡ ። ኢያ፡ ፲፫ ፳፭፥ ፳፬ ፴፫ ። |
| ወፈነወት ዲቦራ ወፀውዓቶ ለባርቅ ወልደ አቤኔሔም እምቃዴስ ዘንፍታሌም ወትቤሎ አኮኑ ኪያከ አዘዘ እግዚአብሔር አምላከ እስራኤል ከመ ትሑር ውስተ ደብረ ታቦር ወንሣእ ምስሌከ እልፈ እደወ እምደቂቀ ንፍታሌም ወእምደቂቀ ዛብሎን ። | ፮ | ዲቦራ ልካ የአቤኔሔምን ልጅ ባርቅን የንፍታሌም ዕጣ ከምትሆን ከቃዴስ አስጠራችው፥ ወደ ደብረ ታቦር ትሄድ ዘንድ የእስራኤል ፈጣሪ እግዚአብሔር አንተን ያዘዘ አይደለምን! ከዛብሎን ልጆችና ከንፍታሌም ልጆች እልፍ ሰዎችን ካንተ ጋራ ይዘህ ሂድ ። ኢያ፡ ፲፱ ፴፮ ። |
| ወእወስደከ ኀበ ፈለገ ቂሶን ላዕለ ሲሳራ መልአከ ሠራዊቱ ለኢያሚን ወሠረገላቲሁ ወብዙኁ ወአገብአ ውስተ እደከ ። | ፯ | በኢያሚን ሠራዊት አዛዥ በሲሳራ ላይ በሠራዊቱና በሠረገላዎቹም ላይ ወደ ቂሶን ወንዝ እወስድኻለሁ በእጅህም እጥለዋለሁ አለችው ። መሳ፡ ፬ ፲፫ ። መዝ፡ ፹፫ ፱ ። |
| ወይቤላ ባርቅ እመ ተሐውሪ ምስሌየ አሐውር ወእመሰ ኢተሐውሪ ምስሌየ ኢየሐውር እስመ ኢየአምር ዕለተ እንተ በቲ ይፌቅድ እግዚአብሔር ይፈኑ መልአኮ ምስሌየ። | ፰ | ባርቅም እግዚአብሔር መልአኩን ከኔ ጋር ይልክ ዘንድ የሚወድበትን ቀን አላውቅምና ከኔ ጋራ ብትሄጂ እሄዳለሁ፥ ከኔ ጋራ ካልሄድሽ ግን አልሄድም አላት ። |
| ወትቤሎ ዲቦራ አሐውር ምስሌከ ወባሕቱ አአምር ከመ ኢይከውነከ ክብረ ዘቀዳሚ ቃልከ በፍኖት እንተ ሖርከ እስመ ውስተ እደ ብእሲት ያገብእ እግዚአብሔር ለሲሳራ፥ ወተንሥአት ዲቦራ ወሖረት ምስለ ባርቅ እምቃዴስ ። | ፱ | ዲቦራም ካንተ ጋር እሄዳለሁ፤ ነገር ግን እግዚአብሔር ሲሳራን በሴት እጅ ይጥለዋልና፥ በሄድክበት ጐዳና የቀደመው ቃልህ ክብር እንዳይሆንህ አውቃለሁ አለችው ዲቦራም ተነሥታ ከባርቅ ጋር ወደ ቃዴስ ሄደች ። |
| ወአዘዞሙ ባርቅ ለዛብሎን ወለንፍታሌም በቃዴስ ከመ ይትልውዎ ወዐርጉ ምስሌሁ እልፍ ብእሲ፥ ወዲቦራሂ ዐርገት ምስሌሁ ። | ፲ | ባርቅም ይከተሉት ዘንድ ንፍታሌምንና ዛብሎንን ወደ ቃዴስ ጠራቸው እልፍም ሰዎች ከርሱ ጋራ ወጡ፥ ዲቦራም ከሱ ጋራ ወጣች ። ዘፀ፡ ፲፩ ፰ ። መሳ፡ ፭ ፲፰ ። |
| ወእለ ቅሩቡ ለቄኔዝ ተፈልጡ እምደቂቀ ኢዮባብ ሐሙሁ ለሙሴ ወኃደረ ትዕይንቱ ኀበ ዕፀ ለበዩት ኀበ ቅሩበ ቃዴስ ። | ፲፩ | የቄኔዝ አቅራቢያዎች የሚሆኑ ሰዎችም ከሙሴ አማት ከኢዮባብ ልጆች ተለዩ፥ ሠራዊቱም በቃዴስ አቅራቢያ (በወይራ) በግራር ዛፍ ሥር አደሩ ። መሳ፡ ፩ ፲፮ ። |
| ወዜነውዎ ለሲሳራ ከመ ዐርገ ባርቅ ወልደ አቤኔሔም ውስተ ደብረ ታቦር ። | ፲፪ | ለሲሳራም የአቤኔሔም ልጅ ባርቅ ወደ ደብረ ታቦር እንደወጣ (ዘመተ) ነገሩት ። ኢያ፡ ፲፬ ፲፪ ። |
| ወአምጽአ ሲሳራ ኵሎ ሠረገላቲሁ እስመ ተስዓቱ ምእት ሠረገላቲሁ ዘሐፂን ቦቱ ወኵሎ ሕዝቢሁ እምአሴሮት ዘሕዛብ ውስተ ፈለገ ቂሶን ። | ፲፫ | ሲሳራ ዘጠኝ መቶ የብረት ሠረገላዎች ነበሩትና ሠረገላዎቹን ሁሉ የአሕዛብ ዕጣ ከምትሆን ከአሴሮት ወደ ቂሶን ወንዝ አመጣ ። መሳ፡ ፮ ፴፬ ። ፪ ሳሙ፡ ፳ ፭ ። |
| ወትቤሎ ዲቦራ ለባርቅ ተንሥእ እስመ ዛቲ ዕለት እንተ በቲ ያገብኦ እግዚአብሔር ለሲሳራ ውስተ እዴከ ወናሁ እግዚአብሔር የሐውር ቅድሜከ፥ ወወረደ ባርቅ እምደብረ ታቦር ወእልፍ ብእሲ ይተልውዎ ። | ፲፬ | ዲቦራም ባርቅን እግዚአብሔር ሲሳራን በእጅህ የሚጥልበት ቀን ይህች ናትና ተነሥ እነሆ እግዚአብሔርም በፊትህ ይሄዳል አለችው፥ ባርቅም እልፍ ሰዎች ተከትለዉት ከደብረ ታቦር ወረደ ። ዘዳ፡ ፱ ፫ ። መሳ፡ ፫ ፳፯ ። |

፲፭ ወአደንገፆ እግዚአብሔር ለሲሳራ ወለኵሉ ሠረገላቲሁ ወለኵሉ ትዕይንቱ ወአውደቆሙ ቅድመ ባርቅ በአፈ ሐፂን ወወረደ ሲሳራ እምላዕለ ሠረገላሁ ወጐየ በእግሩ።

እግዚአብሔር ሲሳራን አስደነገጠው ሠረገላውንም ሁሉ ሠራዊቱንም ሁሉ በባርቅ ፊት በጦር በአፈ ሐፂን ጣላቸው፤ ሲሳራም ከሠረገላ ወርዶ በእግሩ ሸሸ።

፲፮ ወዴገኖ ባርቅ ወተለወ ሠረገላቲሁ ወዴገነ ትዕይንቶ እስከ አኀለቀ አሕዛቢሁ ወሞተ ኵሉ ትዕይንተ ሲሳራ በአፈ ሐፂን ወኢተርፈ ወኢ አሐዱ።

ባርቅም አሳደደው፤ ሠረገላውንም ተከተለ፤ ሠራዊቱን እስኪያጠፋ ድረስ ተከተለ፤ የሲሳራ ሠራዊት ሁሉ በጦር ጠፉ፤ አንድ ሰው ስንኳ አልቀረም።

፲፯ ወሲሳራሰ ጐየ በእግሩ ውስተ ትዕይንተ ኢያኤል ብእሲተ ክቤር ከልአዊ ለቄኔው እስመ ሰላም ውእቱ ማእከሎሙ ለኢያቢን ንጉሠ አሶር ወማእከለ ቤተ ክቤር ቄንያዊ።

ሲሳራ ግን በቄንያው ሰው በክቤር ወገን መካከልና በአሶርያው ንጉሥ በኢያቢን መካከል ፍቅር ነበርና ወደ ቄኔም ወንድም ወደ ክቤር ሚስት ወደ ኢያኤል ሰፈር በእግሩ ሸሸ።

፲፰ ወወፅአት ኢያኤል ወተቀበለቶ ለሲሳራ ወትቤሎ ገኃሥ እግዚእየ ገኃሥ ኀቤየ ወኢትፍራህ ወገኃሠ ኀቤሃ ውስተ ደብተራሃ ወከደነቶ ሠቀ።

ኢያኤልም ወጥታ ሲሳራን ተቀበለችው፤ ጌታዬ! ወደ እኔ ግባ አይዞህ አትፍራ አለችው፤ እሱም ከዚ ዘንድ ወደ ድንኳና ገባ፤ ምንጣፍንም አለበሰችው።

፲፱ ወይቤላ ሲሳራ አስትይኒ ንስቲተ ማየ እስመ ጸማእኩ፤ ወፈትሐት ዝቅዐ ሐሊብ ወአስተየቶ ወከደነቶ ገጾ።

ሲሳራም ጠምቶኛልና ጥቂት ውኃ አጠጪኝ አላት፤ እሷም የወተቱን ጮጮ ክፍታ አጠጣችው ፊቱንም ሸፈነችው። መሳ፥ ፭ ፳፭።

፳ ወይቤላ ቁሚ ኀበ ኆኅተ ደብተራ ወእመቦ ዘመጽአ ኀቤኪ ወይቤለኪ ሀለወኑ ዝየ ብእሲ በሊ አልቦ ወከደነቶ ሠቀ።

በድንኳኑ ደጃፍ ቁሚ፤ ወዳንቺ መጥቶ በዚህ ሰው አለን፤ ብሎ የጠየቀሽ ሰው ቢኖር የለም በይው አላት ምንጣፍንም አለበሰችው።

፳፩ ወነሥአት ኢያኤል ብእሲተ ክቤር መትክለ ደብተራ ወአብነ በክልኤቱ እደዊሃ ወቦአት ወጸቀወቶ ወተከለት ውእተ መትክለ ውስተ መልታሕቱ ወኀደአቶ እስከ ፀመረቶ ምስለ ምድር ወተራገጸ ውእቱ ማእከለ እገሪሃ ወተሠጥሐ ወሞተ።

የክቤር ሚስት ኢያኤልም በአንድ እጇዋ የድንኳን ካስማ፣ በሁለተኛይቱ እጇዋ ደንጊያ ይዛ ገብታ ወግታ ያነን ካስማ በጒንጩ ተከለችው፤ ከምድር ጋር አንድ እስክታደርገው ድረስ መታችው፤ እሱም በእግሯ መካከል ተንፈራፍሮና ተዘርሮ ሞተ።

፳፪ ወበጽሐ ባርቅ እንዘ ይዴግኖ ለሲሳራ ወወፅአት ኢያኤል ወተቀበለቶ ለባርቅ ወትቤሎ ነዓ አርኢከ ብእሴ ዘተኀሥሥ፤ ወቦአ ኀቤሃ ወረከበ ለሲሳራ ወዱቀ በድኖ ወመትክል ውስተ መልታሕቱ።

ባርቅም ሲሳራን እየተከተለ ደረሰ፤ ኢያኤልም ወጥታ ባርቅን ተቀበለችው፤ የምትፈልገውን ሰው ና ላሳይህ አለችው፤ እሱም ወደዚ ገብቶ ሲሳራን ሬሳው ወድቆ ካስማው በጒንጩ ተተክሎ አገኘው።

፳፫ ወአኅሠሮ እግዚአብሔር ለኢያሚን ንጉሠ ከነአን በይእቲ ዕለት በቅድሜሆሙ ለደቂቀ እስራኤል።

እግዚአብሔር በዚያች ቀን በእስራኤል ልጆች ፊት የከነዓን ንጉሥ ኢያሚንን አኰሰሰው።

፳፬ ወሖረት እዴሆሙ ለእግዚአብሔር ምስለ ደቂቀ እስራኤል ወጸንዓት ላዕለ ኢያሚን ንጉሠ ከነዓን እስከ አጥፍኦ።

የእግዚአብሔርም ሥልጣን ከእስራኤል ልጆች ጋር ጸንታ ኖረች፤ እስኪያጠፋውም ድረስ በከነዓን ንጉሥ በኢያሚን ላይ እየጸናች ሄደች።

## ምዕራፍ ፭።

፩ ወኀለየት ዲቦራ በይእቲ ዕለት ቅድመ ባርቅ ወትቤ እንዘ ትኄሊ ሶበ አኀዙ መሳፍንተ እስራኤል በሐሊና ሕዝብ፤ ይባርክዎ ለእግዚአብሔር።

ዲቦራም ስታመሰግን የእስራኤል መሳፍንት የሕዝቡን ልቡና በያዙ ጊዜ እግዚአብሔርን ያመሰግኑታል ብላ በዚያች ቀን በባርቅ ፊት አመሰገነች። ዘፀ፥ ፲፭ ፩።

፪ ስምዑ ነገሥት ወአጽምኡ መኳንንት ጽኑዓን።

ነገሥታቱ ስሙ፤ ጽኑዓን የምትሆኑ መኳንንትም አድምጡ። ዘዳ፥ ፴፪ ፵፪። ፪ ሳሙ፥ ፳፪ ፵፪።

፫ ወአንሰ እኄዝዞ እኄሊ ለእግዚአብሔር አምላከ እስራኤል።

እኔም ለእስራኤል ፈጣሪ ለእግዚአብሔር ምስጋናን ላቀርብ ጀመርሁ (አቀርበለሁ)። መዝ፥ ፪ ፪። ምሳ፥ ፴፩ ፬።

፬ እግዚኦ በፀአትከ እምነ ሴይር ሶበ ተንሥእከ እምሐቅለ ኤዶም፤ ምድር አድለቅለቀት ወሰማይኒ ደንገፀት ወደመናት አንጠብጠቡ ማየ።

አቤቱ! ከሴይር (ከግብጽ) በወጣህ ጊዜ ከኤዶም ምድረ በዳም በተነሣህ ጊዜ ግብጽ ተነዋወጣች፤ ሰማይም ደነገጠች፤ ደመናትም ዝናምን አዘነሙ። ዘዳ፥ ፴፫ ፪።

፭ ወአድባር ተከውሉ እምቅድመ እግዚአብሔር ዝንቱኒ ሲና እምቅድመ እግዚአብሔር አምላከ እስራኤል።

ተራሮችም ከእግዚአብሔር መገለጽ የተነሣ ተነዋወጡ፤ ይህም ደብረ ሲና በእስራኤል ፈጣሪ በእግዚአብሔር ፊት ተነዋወጠ። ዘዳ፥ ፬ ፲፩። ኢሳ፥ ፷፬ ፩-፫።

፮ በመዋዕለ ሴሜጌር ወልደ ቄኔት ወበመዋዕለ ኢያኤል

በኢያኤል ዘመንና በቄኔት ልጅ በሴሜጌር ዘመን ነገ

ኀልቁ ነገሥት ወሖሩ ፍና መብእሰ ወፍኖታተ ፍኖትናተ ።

፯ ወኀልቁ መሬክራን እምእስራኤል እስከ ተንሥአት ዲ
ቦራ ወቆመት እመ ለእስራኤል ።

፰ ወሠምሩ በአማልክተ ከንቱ ከመ ኅብስተ ሰገም ሰበ
ይከድንዎ ውዕዩ አርማኅ ፡ አርባዕቱ እልፍ አርማኅ ።

፱ ልብየሰ ውስተ ዘተአዘዘ ለእስራኤል ፡ ኃያላኒሆሙ
ለእስራኤል ባርክዎ ለእግዚአብሔር ።
፲ እለ ትጼዕኑ ላዕለ አእዱግ ፀዐድዋን ፡ ወትነብሩ ውስተ
ብርሃን ፡ ንቡ ቃለክሙ ።
፲፩ ወሰንቀዉ ማእከለ ብዙኃን ፍሡሓን ወበህየ ይሁቡ
ጽድቀ ለእግዚአብሔር ፡ ጽድቀ ወጽንዐ በውስተ እስራ
ኤል ፡ ወይእተ አሚረ ወረደ ውስተ አህጉሪሁ ሕዝበ እግ
ዚአብሔር ።
፲፪ ተንሥኢ ዲቦራ ወአንሥኢ አእላፈ ምስለ ሕዝብ ተን
ሥኢ ተንሥኢ ምስለ ማኅሌት ፡ ወበኃይል ተንሥእ ባር
ቅ ፡ ወጸንግዎ ዲቦራ ለባርቅ ወጼውዉ ፄዋከ ባርቅ ወልደ
አቤኔሔም ከመ አመ ዓብየ ኃይሉ ።

፲፫ እግዚኦ አድክሞሙ ሊተ ለእለ ይጸንዑኒ ሕዝበ ኤፍ
ሬም ።
፲፬ ወቀሠፎሙ በውስተ ቈላት እኁከ ብንያም በሕዝብከ
እምነ ማኪር ፡ ወወረዱ ይፍትኑ ።
፲፭ ወእምዛብሎን እግዚአብሔር ይጸብእ ሊተ ፡ ወእምኃ
ያላን እምህየ ወትረ በኃይለ ነገር ።
፲፮ ወእምውስተ ይሳኮር ምስለ ዲቦራ ፈነወ አጋራኒሁ
ውስተ ቈላት ከመ ትንበር አንተ ማእከለ ከናፍር ወሰፍሐ
በእገሪሁ ነፍቆ ሮቤል ዓቢይ ጥይቅና ልቡ ።
፲፯ ወለምንት ለከ ትነብር ምስለ መስፌተም ከመ ታጽ
ምእ ከመ ይትፋጸዩ እለ ይነሥኡ ከመ ይኅልፉ ውስተ
ዘሮቤል ።
፲፰ ዓቢይ አሠረ ልቡ ለጋድ ውስተ ማዕዶተ ዮርዳኖስ
ኀደረ ፡ ወዳን ለምንት ይነብር ውስተ አሕማር ወአሴርሰ
ነበረ ውስተ ሐይቀ ባሕር ወውስተ ወሰኑ ነበረ ።
፲፱ ዛብሎን ሕዝብ ዘአየረ ነፍሶ ለሞት ወንፍታሌም ው
ስተ መልዕልተ ሐቅል ።
፳ ወመጽኡ ነገሥት ወተቃተሉ ወይእተ አሚረ ተቃ
ተሉ ነገሥተ ከነአን በቶናኅ በኀበ ማየ መጌዶ ወኢነሥእ
በትዕግልት ብሩረ ።
፳፩ ወበሰማይ ተፃብኡ ከዋክብት እምቀትሎሙ ወተቃ
ተሉ ምስለ ሲሳራ ።
፳፪ ወአውፅኦሙ በፈለገ ቂሶን ወፈለገ ቂሔሜን ወተቃ
ተሉ በፈለገ ቂሶን ነፍስየ ጽንዒ ።
፳፫ ወይእተ አሚረ ተቀጥቀጠ ሰኰና አፍራሲሆሙ ለአ
ምዳሮት ወኀያላኒሁ ለማዘር ይረግምዎ ።
፳፬ ወይቤ መልአከ እግዚአብሔር በመርገም ርግምዎሙ

ሥቃት አለቁ ፡ የተሰነካከሉና ግልብጥብጥ ያሉ ጐዳናዎ
ችንም ሄዱ ። መሳ፡ ፫ ፴፩ ፡ ፬ ፲፯ ።
ዲቦራ እስክትነሣ ድረስና ለእስራኤልም እናት ሁና
እስክትተካ ድረስ ከእስራኤል ሕልምን የሚተረጕሙ
ሰዎች ጠፉ ። መሳ፡ ፭ ፲፩ ።
ከንቱ የሆኑ ጣኦታትን ወደዱ ፡ የገብስ እንጀራ በከዱ
ኑት ጊዜ ከሸልሸል ብሎ እንዲያር ለእስራኤል በታዘዘ
ረድኤት በለሽፋፍ ዘገርን የያዙ አራት እልፍ (ጦሮች)
ኃያላን ጠፉ ። ዘዳ፡ ፴፪ ፲፯ ። መሳ፡ ፪ ፲፪ - ፲፯ ።
ልቤ ወደ እስራኤል አለቆች ነው ፡ የእስራኤል መኳ
ንንትም እግዚአብሔርን አመስግኑት ።
በነጫጮች አህዮች የምትቀመጡም በተድላ ደስታ
የምትኖሩም ሰዎች በቃላችሁ ተናገሩ ። ዘኍ፡ ፳፪ ፳፩ ።
ደስ በላቸው ሰዎች መካከል መሰንቆን ምቱ ፡ በዚያ
ለእግዚአብሔር እውነተኛ ምስጋናን ያቀርባሉ በእስራኤል
ዘንድ ጽናትንና እውነትን ያቀርባሉ ፡ በዚያን ጊዜም የእ
ግዚአብሔር ወገን ወደ አገሩ ወረደ ። ዘፍ፡ ፳፬ ፲፩ ።
ዲቦራ ተነሺ ፡ አእላፈ ዛብሎንን ከአእላፈ ይሳኮር ጋራ
አንሺ ከምስጋና ጋራ ተነሺ ተነሺ ባርቅም በኃይል ተነ
ሣ ፡ ዲቦራ ባርቅን አጽኚው የእግዚአብሔር ኃይሉ በተገ
ለጠ ጊዜ እንደ ተገለጠልህ መጠን የአቤኔሔም ልጅ ባርቅ
ምርኮህን ማርክ ።
አቤቱ ፤ በኔ የሚጸኑብኝን የኤፍሬምን ወገን አድክ
ምልኝ ።
ወንድምህ በአውራጃ አጠፋቸው ፡ ብንያም በወገንህ
አፍራሰሁ ፡ ይዘርፉ ዘንድ ከማኪር ወረዱ ።
እግዚአብሔር በኃያላኑ አድሮ ወትሮ በሚነገር ነገር
ከዛብሎን ያጠፋልኛል ። ዘዳ፡ ፴፫ ፳፩ ።
ከነገደ ይሳኮርም ከዲቦራ ጋራ አርበኞችን ላክ ፡ በወን
ድሞችህ መካከል ትቀመጥ ዘንድ ምን አለህ ፤ እግሩን አን
ፈራጠ ቀረ ፡ የሮቤል የልቡ ዕውቀት ደግ ነበር ።
በነገደ ሮቤል ዕጣ ይሄዱ ዘንድ ገድለው ሲደነፉ ትሰማ
ዘንድ ከመስፌተም (ከሳፊታዎች) ጋራ ለምን ትኖራለህ ፤ ።

የጋድ የልቡ ዕውቀት ደግ ነበር ፡ በዮርዳኖስ ማዶ ቀረ
ጋድ መርከቦች በወደብ እንዲኖሩ ከነገዶች ጋራ ለምን
ተቀመጠ ፤ አሴር ግን በባሕር ዳርቻ ባለ በወሰኑ ኖረ ።
ዛብሎን ሰውነቱን ለሞት የሰጠ ወገን ነው ፡ ንፍታሌ
ምም በበረኻው በአገሩ ይኖራል ። መሳ፡ ፬ ፲ ።
ነገሥታቱም ወጥተው ተዋጉ ፡ የዚያን ጊዜ የከነዓን
ነገሥታት የመጌዶ ውኃ ባለበት በቶናህ ተዋጉ ፡ ብርቅ
ብርን ቀምቶ አልወሰደም ። ኢያ፡ ፲፪ ፳፩ ።
ከሰልፋቸው የተነሣ እስራኤል በደብረ ታቦር ተዋጉ ፡
ከሲሳራም ጋር ተዋጉ ።
ወደ ቂሔሜን ወንዝና ወደ ቂሶን ወንዝ አወጣቸው ፡
በቂሶን ወንዝም ተዋጉ ፡ ሰውነቴ ጽኚ ። መሳ፡ ፬ ፯ ።
የዚያን ጊዜ የአምዳሮች የፈረሶቻቸው ሰኰና አኰበ
ኰበ የአሕዛብ አርበኞች (ማዘርን) ጣኦቱን ይረግሙታል ።
ከእግዚአብሔር የተላከው መልአክም ጽኑዓን ከሆኑ አር

ለእለ ውስተ አብያቲሃ እስመ ኢመጽኡ ውስተ ረድኤተ እግዚአብሔር እመስተቃትላን ጽኑዓን ።

፳፭ ቡርክተ ትኩን እምነ አንስት ኢያኤል ብእሲተ ክቤር ቄንያዊ እምነ አንስት ቡርክት በውስተ ደብተራ ።

፳፮ ማየ ሰአላ ወሐሊበ ወሀበቶ ወበአይገን ዐቢይ አቅረ በት ሎቱ ዕቋነ ።

፳፯ ወበእዴሃ እንተ ጸጋም ተመጠወት መትከለ ወበየማና ጕድአተ ወቀተለቶ ለሲሳራ ወቀጥቀጠቶ ርእሶ ወደመቀቶ መልታሕቶ ።

፳፰ ወተራገጸ በማእከለ እገሪሃ ወበጎበ ተራጋጸ በህየ ኀሠረ ።

፳፱ ወእንተ መስኮት ትሔውጽ እሙ ለሲሳራ እንተ ሰቅ ሰቅ ትሬኢ እመ በ ዘገብአ እምኀበ ሲሳራ ወበበይነ ምንት ተድኅረ ሠረገላሁ ለሲሳራ በጺሐ ወበበይነ ምንት ጐንደየ እግረ ሠረገላቲሁ ጠቢበት ።

፴ ወሳእከቲሃ ላቲ አውሥአሃ ወእማንቱሰ አውሥአሃ በከመ ቃላ ።

፴፩ እኮኑ ረከበሁ እንዘ ይከፍል ምኅርከ ወይትዓረክ እዕርክተ በላዕለ አርእስቲሆሙ ለኀያላን፤ ወበርበረ ውእቱ ሲሳራ በርበረ ኅብር፣ ወዘዘዚአሁ ጥምዐተ ኅበሪሁ ወእሥቀ ውስተ ክሳዱ ዘበርበረ ።

፴፪ ከማሁ ለይትኀጐሉ ኵሎሙ ፀርከ እግዚአ ወእለሰ ያፈቅሩከ ከመ ሠርቀ ፀሐይ በኀይሉ ወአዕረፈት ምድር አርብዓ ዓመተ ።

ምዕራፍ ፮ ።

፩ ወገብሩ ደቂቀ እስራኤል እኩየ ቅድመ እግዚአብሔር ወአግብኦሙ እግዚአብሔር ውስተ እደ ምድያም ሰብዐተ ዓመተ ።

፪ ወጸንዐት እዴሆሙ ለምድያም ላዕለ እስራኤል ወገብሩ ሎሙ ደቂቀ እስራኤል እምቅድመ ምድያም በዓታተ ወአጽዋናተ ውስተ አድባር ወውስተ አጽዳፍ ።

፫ ወእምዝ ሶበ ይዘርኡ ሰብአ እስራኤል የዐርጉ ምድያም ወአማሌቅ ወደቂቀ ጽባሕ የዓርጉ ላዕሌሆሙ ።

፬ ወይትዐየኑ ዲቤሆሙ ወያማስኑ ፍሬ ገራውሂሆሙ እስከ ይበጽሑ ውስተ ጋዛን ወኢያተርፉ ሎሙ ወኢምንተ በዘየሐይዉ ለእስራኤል ወመራዕይሆሙኒ ወላሕሞሙኒ ወአድጎሙኒ ።

፭ እስመ የዐርጉ ላዕሌሆሙ እሙንቱ ወእንስሳሆሙ ወተዓይኒሆሙ ያመጽኡ ወይበጽሕዎሙ ወከመ አንበጣ ብዝኆሙ ወአልቦሙ ኊልቈ ኢእሙንቱ ወኢአግማላቲሆሙ ወይመጽኡ ውስተ ምድረ እስራኤል ከመ ያማስንዎሙ ።

በኖች ጋራ እግዚአብሔር ወደ ሚያደርግላቸው ረድኤት አልመጡምና በቤቶቿ የሚኖሩ ሰዎች ርግማንን ርገሚቸው አለ ። ነህ፡ ፫ ፭ ። ፩ ሳሙ፡ ፩ ፲፮ ።

የቄንያዊው የክቤር ሚስት ኢያኤል ከሴቶች ተለይታ የከበረች ትሁን በድንኳን ውስጥ ከሚኖሩ ሴቶች ይልቅ የተባረከች ትሁን ። መሳ፡ ፬ ፲፯ ።

ውኃን ለመናት ወተትን ሰጠችው በታላቅ መንቀልም መግሜትን አቀረበችለት ። መሳ፡ ፬ ፲፱ ።

በግራ እጅዋ ከስማውን ተቀብላ፣ በቀኝ እጅዋ መዶሻ ሲሳራን ገደለችው፣ ራሱንም ከሰከሰችው ጉንጩንም ሰፋ ለቀችው ። መሳ፡ ፬ ፳፩ ።

በእግሯ መካከል ተንፈራፈረ፣ በተንፈራፈረበትም በታ ተዋረደ ተገሰቀሰ (ሞተ) ።

የሲሳራ እናት በሰገነት ሁና ከሲሳራ ዘንድ የተመለሰ አለ እንደሆነ ብላ በመስኮት ትመለከት ነበር፣ የሲሳራም ሠረገላ ወደቢ ከመድረስ ስለምን እንደ ዘገየ፣ ቀላሎች የ ሆኑ የሠረገላዎቹ እግሮችም እንደምንም እንደ ዘገዩ ታይ ዘንድ በመስኮት ትመለከት ነበር ። ዘፀ፡ ፴፪ ፳ ።

ገረዶቿም መለሱላት፣ እነሳቸው ግን እንደ ቃሏ መለ ሱላት ።

ብዙ ምርኮ አግኝተዋልና ምርኮውን ሲያከፍል የኃያ ላኑን ቸብቸበ እየቈረጡ እየሰጡት በወዳጅ ላይ ወዳጅ ሲገ ዛ ሲሳራም ምርኮውን ማርኮ አበላሉ አጠላለቁ ልዩ የሆኑ አራት ኅብር አምስት የወርቀ ዘበ ግምጃ ሲሸልም የማረከ ውን ዝርግፍ በአንገቱ ሲያስር ይሆናል ብለው እንደ ቃሏ መለሱላት ።

አቤቱ! ጠላቶችህ ሁሉ እንደሱ ይጥፉ፣ የሚወዱህ ሰዎች ግን በኃይሉ እንደሚወጣ እንደ ፀሐይ ብርሃን ይ ሁኑ አለች፣ ምድርም አርባ ዘመን አረፈች።

ምዕራፍ ፮ ።

፩ የእስራኤል ልጆች በእግዚአብሔር ፊት ክፉ ሥራን ሠሩ፣ እግዚአብሔርም ሰባት ዓመት በምድያም እጅ ጣላቸው ።

፪ የምድያም ሥልጣንም በእስራኤል ላይ ጸናች፣ የእስ ራኤልም ልጆች ከምድያም ፊት በገደሎች ላይና በተራ ሮች ላይ አምባዎችንና ዋሻዎችን ሠሩ ።

፫ ከዚህ በኋላ እስራኤል ዘር በዘሩ ጊዜ አማሌቅና የም ድያም ሰዎች በምሥራቅ ያሉ ልጆችም ወደነሳቸው ዘመቱ።

፬ በነሳቸውም ላይ ይሰፍሩ ነበር፣ ወደ ጋዛን እስኪደ ርሱ ድረስ ደርሰው አዝመራቸውን ያጠፉባቸው ነበር፣ እስራኤል በሚድኑ ገንዘብ ምንም ምን አያስቀሩላቸውም ነበር፣ መንጋዎቻቸውንም ሆነ፣ ላሞቻቸውንና አህያዎ ቻቸውንም ሆነ ።

፭ እነሱ በነሳቸው ላይ ይዘምቱ ነበር፣ ከብቶቻቸውንና ሠራዊቶቻቸውን ይዘው ይመጡባቸው ነበር፣ ብዛታቸ ውም እንደ አንበጣ ነበር፣ ለነሳቸውም ሆነ ለግመሎቻ ቸው ስፍር ቊጥር አልነበራቸውምና ያጠፉዋቸው ዘንድ ወደ እስራኤል አገር ይመጡ ነበር ። መሳ፡ ፮ ፲፱ ።

ኢሎፍሊ ይኴንኑነ ለምንት ከመዝ ገበርከ ላዕሌነ ፡ ወይቤ-
ሎሙ ሶምሶን በከመ ገብሩ ላዕሌከሙ ከማሁ ገበርኩ
ላዕሌሆሙ ።
፲፪ ወይቤልዎ ከመ ንእስርከ ወረድነ ወናገብእከ ውስተ
እደዊሆሙ ለኢሎፍሊ ፡ ወይቤሎሙ ሶምሶን መሐሉ ሊተ
አንትሙ ከመ ኢትቀትሉኒ ወአግብኡኒ ሎሙ ወአንት
ሙሰ ኢትትራከቡ ምስሌየ ወመሐሉ ሎቱ ።
፲፫ ወይቤልዎ አልቦ ዳእሙ ነአስረከ በማእሰር ወናገብእከ
ውስተ እደዊሆሙ ወቀቲለሰ ኢንቀትለከ ፡ ወአሰርዎ በክል
ኤቱ መፃምድ ሐዲሳት ወአውፅእዎ እምይእቲ ኰኵሕ ።
፲፬ ወበጽሐ እስከ ኀበ ዐጽመ መንከሰ አድግ ወወውዑ
ኢሎፍሊ ወተቀበልዎ ወሮጹ ኀቤሁ ፡ ወመጽአ ላዕሌሁ
መንፈሰ እግዚአብሔር ወኮኑ እልክቱ መፃምድ እለ ውስ
ተ መዝራዕቱ ከመ ሰበ ያጼኑ ኀሠር እሳተ ወተፈትሐ ማእ
ሚሁ እመዝራዕቱ ።
፲፭ ወረከበ ዐፅመ መንሰከ አድግ ግዱፈ ውስተ ፍኖት
ወአትሐተ እዴሁ ወተመጠውዋ ወቀተለ ባቲ ዐሠርተ ም
እተ ብእሴ ።
፲፮ ወይቤ ሶምሶን ፡ በዐፅመ መንሰከ አድግ ቀተልኩ ዐሠ
ርተ ምእተ ብእሴ ።
፲፯ ወእምዝ ሰበ አኅለቀ ነቢበ ገደፋ ለይእቲ ዐፅመ መን
ስከ እምእዴሁ ወሰመዮ ለውእቱ መካን ቀትለ ዐፅመ
መንስከ ።
፲፰ ወጸምአ ጥቀ ወጸርሐ ኀበ እግዚአብሔር ወይቤ ፡ አን
ተ አግባእከ ውስተ እደ ገብርከ ዘንተ ሕይወተ ዐቢየ ወይ
እዜሰ እመውት በጽምእ ወእወድቅ ውስተ እደዊሆሙ ለቈ
ላፋን ።
፲፱ ወአርኀወ እግዚአብሔር ንቅዐታ ለይእቲ ዐፅመ መን
ስከ ወወፅአ እምኔሃ ማይ ወሰትየ ወገብአት ነፍሱ ወአፅ
ረፈ ፡ ወበበይነ ዝንቱ ተሰምየ ስሙ ለውእቱ መካን ነቅዐ
ዐፅመ መንከስ እስከ ዮም ።
፳ ወኰነኖሙ ለእስራኤል በመዋዕለ ኢሎፍሊ ዕሥራ
ዓመተ ።

ምዕራፍ ፲፮ ።

፩ ወሖረ ሶምሶን እምህየ ውስተ ጋዛ ወርእየ በህየ ብእ
ሲተ ዘማ ወቦአ ኀቤሃ ።
፪ ወነገርዎሙ ለሰብአ ጋዛ ወይቤልዎሙ ፡ መጽአ ሶም
ሶን ዝየ ፡ ወዖድዎ ወዐገትዎ ኵላ ሌሊተ ውስተ አንቀጸ
ሀገር ፡ ወጸንሑ ኵላ ሌሊተ ወይቤሉ ፡ ንጸንሖ ኵላ ሌሊ
ተ ወንቀትሎ በጽባሕ ።
፫ ወኖመ ሶምሶን እስከ መንፈቀ ሌሊት ወተንሥአ ሶም
ሶን በመንፈቀ ሌሊት ወአኀዘ ሊኖኀተ ሀገር ዘአንቀጽ በክ
ልኤሆን ራግዛቲሃ ወፆሮሙ ምስለ ኵሉ ሰብኡ ወተሰ
ከመ ላዕለ መትከፍቱ ፡ ወአዕረጎሙ ላዕለ ርእሰ ደብር ዘቅ
ድመ ኬብሮን ወአንበሮሙ ህየ ።
፬ ወእምድኅረ ዝንቱ አፍቀረ ብእሲተ በኀበ ፈለገ ሦራኅ
ወስማ ደሊላ ።

ምን በኛ ለምን እንዲህ አደረግህ ፡ አሉት ፡ ሶምሶንም በና
ንተ እንዳደረጉብቻሁ እኔም በነሳቸው እንደዚያው አደረ
ግሁባቸው አላቸው ። መሳ፡ ፲፭ ፲፪ ፡ ፲፬ ፱ ።
እስረን ለኢሎፍላውያን እንሰጥህ ዘንድ ወረድን አሉ
ት ፤ ሶምሶንም እናንተ እንዳትገድሉኝ ማሉልኝ ፡ ለነሱ
አሳልፋችሁ ስጡኝ እናንተ ግን እኔን በጠብ አትገናኙኝ
አላቸው ፡ እነሱም ማሉለት ።
በእግር ብረት አስረን እንሰጥሃለን እንጂ የምንተውህ
አይደለም መግደል ግን አንገድልህም አሉት ፡ በሁለትም
አዲስ ገመድ አስረው ከዚያች አለት አወጡት ።
የአህያ ምንጋጋ አጥንት ወዳለበት ቦታ ደረሰ ፡ ኢሎ
ፍላውያንም ደንፍተው ተቀበሉት ፡ ወደሱም ሮጡ ፡ በሱ
ም የእግዚአብሔር መንፈስ ረድኤት አደረበት ፡ በክንዱ
ያሉ ላመ ገመዶችም ገለባ እሳት በበላው ጊዜ እንዲያርር
እርር ኩምትር አሉ እስራቱም ከክንዱ ተፈታ ።
ያህያ ምንጋጋ አጥንት በጉዳና ወድቆ አገኘ ፡ እጁን
ዝቅ አድርጎ አነሳት በዚያችም ሺሕ ሰዎችን ገደለባት ።
ዘሌዋ፡ ፳፮ ፰ ። ኢ.ያ፡ ፳፫ ፲ ። ኢ.ሳ፡ ፩ ፯ ።
ሶምሶን በአህያ ምንጋጋ አጥንት ሺሕ ሰዎችን ገደ
ልኩ አለ ። መሳ፡ ፫ ፴፩ ።
ከዚህ በኋላ ይህን ተናግሮ በፈጸመ ጊዜ ያችን የአህያ
ምንጋጋ አጥንት ከእጁ ጣላት ፡ ያነንም ቦታ ስሙ የአህያ
ምንጋጋ አጥንት ሰልፍ የተደረገበት አለው ።
ውኃን እጅግ ተጠማ ፡ ወደ እግዚአብሔርም ጮኸ ፡
ይህን ታላቅ ድኅነት በኔ በባርያህ እጅ አደረግህ አሁን ግን
በውኃ ጥም እሞታለሁ ፡ በነዚህም በቈላፋን እጅ እወድ
ቃለሁ አለ ። ዘፍ፡ ፵፭ ፳፤ ። መሳ፡ ፲፪ ፲፯ ።
እግዚአብሔርም ከዚያች ከአህያ ምንጋጋ ውኃን አፈ
ለቀለት ፡ ያነንም ጠጥቶ ነፍሱ ተመልሳለት ከውኃ ጥም
ዐረፈ ፡ ስለዚህ የዚያ ቦታ ስሙ እስካሁን ድረስ ከአህያ
ምንጋጋ ውኃ የፈለቀበት ተባለ ። መሳ፡ ፲፭ ፱ ።
በኢሎፍላውያንም ዘመን እስራኤልን ሃያ ዘመን
ገዛቸው ። መሳ፡ ፲፫ ፩ ።

ምዕራፍ ፲፮ ።

ሶምሶን ከዚያ ወደ ጋዛ ሄደ ፡ በዚያም ጋለሞታ ሴት
አይቶ ወደርሷ ገባ ፡ (ደረሰባት) ። መሳ፡ ፲፯ ፳፩ ።
ለጋዛም ሰዎች ሶምሶን ወደዚህ መጣ ብለው ነገሩዋ
ቸው ፡ በከተማውም በር መላ ሌሊቱን ሁሉ ከብበው ሲጠ
ብቁት አደሩ ፡ ሌሊቱን ሁሉ ስንጠብቀው አድረን ጧት
እንገድለው አሉ ። ዮሐ፡ ፱ ፳፱ ።
ሶምሶንም እኩለ ሌሊቱ እኩሌታ ድረስ ተኛ ፡ በሌሊ
ቱም እኩሌታ ተነሥቶ በከተማው በር ያሉ የመጠበቂያ
ውን ደጃፍ ሁለቱን መቃን መድረኩን ያዘ ፡ ከሰዎቹ ሁሉ
ጋራ በትከሻው ተሸከሞ በኬብሮን አንጻር ወዳለ ተራራ
አውጥቶ በዚያ አፈሰሳቸው ።
ከዚህም በኋላ በሦራሕ ወንዝ አጠገብ ያለች ሴትን ወ
ደደ ፡ ስሟም ደሊላ ይባላል ። ዘፍ፡ ፵፱ ፲፭ ።

፭ ወዐርጉ ኀቤሃ መሳፍንተ ኢሎፍሊ ፡ ወይቤልዋ አስ ፍጢዮ ወአእምሪ በምንት ዓብየ ኃይሉ ወበምንት ንክሎ ወንአስሮ ከመ ናድክሞ ፡ ወንሁበኪ ንሕነ ዓሠርቱ ምእት ብእሲ ዓሠርተ ምእተ ብሩረ ።

የኢሎፍሊ ሹማምንትም ወደርሷ ወጥተው አባብሊ ልን ፡ ጽኑ የሆነ ኃይሉ በምን ፤ እንደሆነ በምንም እንድን ችለውና እናደክመው ዘንድ በምንም እንድናስረው ዕወቂ እኛ ሺው ሰዎች ሺሕ ብር እንሰጥሻለን አሏት ።

፮ ወትቤሎ ደሊላ ለሰምሶን አይድዐኒ ምንት ውእቱ ኃይ ልከ ዓቢይ ወበምንት እመ አሰሩከ ትደክም ።

ደሊላም ሶምሶንን ኃይልህ ጽኑ መሆኑ በምን እንደ ሆነ ንገረኝ፡ በምንስ ቢያስሩህ ትደክማለህ ፤ አለችው ።

፯ ወይቤላ ሶምሶን እመ አሰሩኒ በሰብዐቱ አውታር ሐዲ ሳት እለ አልበሙ ብትከት እደክም እንከ ወእከውን ከመ አሐዱ እምእጓለ እመሕያው ።

ሶምሶንም በሰባት ባልደረቀ እርጥብ ጠፍሮች ቢያ ስሩኝ እደክማለሁ ከሰውም እንደ አንዱ እሆናለሁ አላት። ኢዮብ ፴ ፲፩ ፡ መዝ፡ ፲፩ ፪ ። ሕዝ፡ ፴፮ ፳፱ ።

፰ ወአምጽኡ ላቲ መሳፍንተ ኢሎፍሊ ሰብዐተ አውታረ ሐዲሳተ እለ አልበሙ ብትከት ወአሰረቶ በሙ ።

የኢሎፍሊም ሹማምንት አዲሶች የሆኑ መቁረጥ የሌ ለባቸው ሰባት አውታሮችን አመጡላት፡ በነሳቸውም አሰረችው ።

፱ ወእለሰ ይጸንሕዎ ይነብሩ ውስተ ውሣጢት ወትቤሎ መጽኡከ ኢሎፍሊ ሶምሶን ፡ ወበተኮሙ ለእሎንቱ አው ታር ከመ ይትበተክ ፈትል ሶበ ያጼኑ እሳተ ወኢተዐውቀ ኀይሉ ።

የሚጠብቁት ሰዎች ግን በውስጥ ነበሩ ፡ እርሷም ሶም ሶን ! ኢሎፍላውያን መጡብህ አለችው ፤ እነዚያንም አው ታሮች ፈትል እሳት በሸተተው ጊዜ እንዲቈረጥ ቈረጣ ቸው የአውታሩም ኃይል አልታወቀም ።

፲ ወትቤሎ ደሊላ ለሶምሶን ፡ ናሁ አስተሐቀርከኒ ወሐ ሰተ ተናገርከኒ፡ ወይእዜኒ አይድዐኒ በምንት የአስሩከ ።

ደሊላም ሶምሶንን እነሆ ሸነገልከኝ ሐሰት ነገርን ነገ ርከኝ፡ አሁንም እውነቱን ንገረኝ በምን ቢያስሩህ ነው ኃይልህ የሚደክመው ፤ አለችው ።

፲፩ ወይቤላ እመ አሰሩኒ በሰብዐቱ መፃምድ እለ ኢገብሩ በሙ ግብረ እደክም እንከ ወእከውን ከመ አሐዱ እምነ እጓለ እመሕያው ።

ሥራ ባልሠሩባቸው በሰባት ገመዶች ቢያስሩኝ ከዚህ በኋላ እደክማለሁ፡ ከሰውም አንዳንዱ እሆናለሁ አላት ። መሳፍ፡ ፲፭ ፲፫ - ፲፬ ፡ ፲፮ ፯ - ፲፯ ።

፲፪ ወነሥአት ደሊላ ሰብዓተ መፃምደ ሐዲሳተ ወአሰረቶ በሙ ፡ ወትቤሎ ኢሎፍሊ መጽኡከ ሶምሶን ፡ ወእለሰ ይጸ ንሕዎ ይነብሩ ውስተ ውሣጢት ወበተኮሙ እመዝራዕቱ ከመ ፈትል ።

ደሊላም ሰባት አዳዲስ ገመዶች አምጥታ በነሱ አሰራ ሶምሶን ! ኢሎፍላውያን መጡብህ ፤ አለችው ፡ የሚጠብ ቁት ሰዎች ግን በውስጥ ነበሩ ከክንዱም እንደ ፈትል ቈረጣቸው ።

፲፫ ወትቤሎ ደሊላ ለሶምሶን ፡ ወይእዜኒ አስተሐቀርከኒ ወሐሰተ ተናገርከኒ ወኢያይዳዕከኒ አይድዐኒ እንከሰ በም ንት የአስሩከ ።

ደሊላም ሶምሶንን አሁንም ሸነገልከኝ ሐሰት ነገርን ም ነገርከኝ፡ እውነቱን አልነገርከኝም እንግዲህ እውነ ቱን ንገረኝ በምን ቢያስሩህ ኃይልህ ይደክማል ፤ አለችው።

፲፬ ወይቤላ እመ ፀፈርኪዮን ለሰብዑ ቈናዝዐየ ዘርእስየ ወተከልክዮን በሰብዐቱ መታክል ውስተ አረፍት እደክም እንከ ወእከውን ከመ አሐዱ እምእጓለ እመሕያው ።

በራሴ ያሉ ሰባቱን ብርንጕዎች (ጕንጕኖች) አስረሽ በኖራው ላይ በሰባት ካስማዎች ብታስመቺያቸው ከዚያ በኋላ ኃይሌ ይደክማል ፡ ከሰውም እንደ አንዱ እሆናለሁ አላት።

፲፭ ወአኖመቶ ደሊላ ወፀፈረቶን ለሰብዑ ቈናዝዒሁ ዘር እሱ በኃይል ወተከለቶን በመታክል ውስተ አረፍት ፡ ወት ቤሎ መጽኡከ ኢሎፍሊ ሶምሶን ፡ ወነቅሐ እምንዋሙ ወነዝዐ ውእቱ መታክለ እምነ አረፍት ምስለ ቈናዝዒሁ ወኢተዐውቀ ኃይሉ ።

ደሊላም አስተኝታ በራሱ ላይ ያሉ ሰባቱን ብርንጕዎ ቹን በኃይል አሰረቻቸው በኖራው ላይ በካስማ አስመታቻ ቸው ሶምሶን ኢሎፍላውያን መጡብህ ፤ አለችው ፡ ከእን ቅልፉም ተነሥቶ ያነን ካስማ ከብርንጕዎቹ (ከቆንዳላዎቹ) ጋራ ከኖራው (ከግድግዳው) ነቀለው ኃይሉም የሚደክም በት አልታወቀም ። መሳ፡ ፬ ፳፩ ።

፲፮ ወትቤሎ ደሊላ፣ እፎ ትቤለኒ አፍቀርኩኪ ወልብየ ምስሌኪ ወናሁ ሣልስ ዝንቱ እንዘ ታስተሐቅረኒ ወኢታ የድዐኒ በምንት ውእቱ ኀይልከ ዐቢይ ።

ደሊላም እወድሻለሁ ልቤም ካንቺ ጋር ነው ለምን ትለኛለህ እነሆ ስትሸነግለኝ ይህ ሦስተኛህ ነው ፡ ኃይልህ ጽኑ መሆኑ ፡ በምን እንደሆነ አልነገርከኝም ፤ አለችው ።

፲፯ ወእምዝ ሶበ አሥርሐቶ በነቢብ ኵላ ሌሊተ አጽሐ በቶ እስከ ተቈጥዐ ለሞት ።

ከዚህ በኋላ መላ ሌሊቱን በነገር ባደከመችው ጊዜ ሊሞት ብሎ እስኪበሳጭ ድረስ ዘበዘበችው ።

፲፰ ወአይድዓ ኵሎ ዘውስተ ልቡ ወይቤላ መላጺ ኢለከ ፈኒ ርእስየ ፡ እስመ ናዝራዊ አነ ለእግዚአብሔር እምከርሠ እምየ ወእምከመ ተላጸይኩ የኀድገኒ ኀይልየ ወእደክም ወእከውን ከመ ኵሉ እጓለ እመሕያው ።

በልቡ ያለውን ሁሉ ነገራት ፡ እኔ ለእግዚአብሔር የስ ለት ልጅ ነኝና ከናቴ ማኅፀን ከተወለድኩ ጀምሮ ምላጭ ራሴን አልነካኝም ፡ ጠጕሬን ከተላጨሁ ኃይሌ ይነሣል ፡ እደክማለሁ ፡ ከሰው እንደ አንዱ እሆናለሁ አላት ።

፲፱ ወአእመረት ደሊላ ከመ አይድኃ ኵሎ ዘውስተ ልቡ ወለአከት ወጸውዓቶሙ ለመላእክተ ኢሎፍሊ እንዘ ትብል ንዑ አሐተ ዕርጐ እስመ አይድዐኒ ኵሎ ዘውስተ ልቡ ወዐርጉ ኀቤሃ ኵሎሙ መሳፍንተ ኢሎፍሊ ወአምጽኡ ወርቀ ምስሌሆሙ ።

፳ ወአኖመቶ ማእከለ ብረኪሃ ወጸውዐት ቀሪጼ ወቀረጸቶን ለሳቡዕ ቍናዝወ ርእሱ ወአኀዘ ይድክም ወኀደጎ ኃይሉ ።

፳፩ ወትቤሎ ደሊላ መጽኡከ ኢሎፍሊ ሶምሶን፣ ወነቅሐ እምንዋሙ ወይቤ እወፅእ ወእገብር ከመ ዘልፍ ወእነፅሕሙ ወውእቱሰ ኢያእመረ ከመ ኀደጎ እግዚአብሔር ።

፳፪ ወአኀዝዎ ኢሎፍሊ ወአውፅኡ አዕይንቲሁ ወአውረድዎ ውስተ ጋዛን ወሞቅሕዎ በመዋቅሕተ ሐፂን ወአንበርዎ ውስተ ቤተ ሞቅሕ ይሐርጽ ።

፳፫ ወአኀዘ ሥዕርቱ ይብቍል እምዘቀረፅዎ ።

፳፬ ወተጋብኡ መላእክተ ኢሎፍሊ ከመ ይሡዑ መሥዋዕተ ለአምላኮሙ ወከመ ይትፌሥሑ፣ ወይቤሉ አግብአ አምላክነ ለሶምሶን ፀርነ ውስተ እዴነ ።

፳፭ ወሰበ ርእይዎ ሕዝብ አእኰትዎ ለአምላኮሙ ወይቤሉ አግብአ አምላክነ ለፀርነ ውስቴ እዴነ ዘአማሰና ለምድርነ ወአብዝኀ አብድንቲነ ።

፳፮ ወእምዝ ሰበ ተፈሥሑ ይቤሉ ጸውዕዎ ለሶምሶን እምነ ቤተ ሞቅሕ ይትዌነይ በቅድሜነ፣ ወጸውዕዎ ለሶምሶን እምነ ቤተ ሞቅሕ ወተሣለቁ ላዕሌሁ ወአቀምዎ ማእከለ ክልኤቱ አዕማድ ።

፳፯ ወይቤሎ ሶምሶን ለወልድ ዘይመርሖ አዕርፈኒ ወአግሥሥኒ አዕማደ እለ ዲቤሆን ይቀውም ዝንቱ ቤት ወእስምከኒ ላዕሌሆን ወንብረ ሎቱ ውእቱ ወልድ ከማሁ ።

፳፰ ወመልኡ ውስተ ውእቱ ቤት እድ ወአንስት ወሀለዉ ሀየ ኵሎሙ መሳፍንተ ኢሎፍሊ ውስተ ናሕስኒ ወየአክሉ ሠላሳ ምእተ እደው ወአንስተ ከመ ይነጽርዎ ለሶምሶን ከመ ይትዌነይ ።

፳፱ ወጸርሐ ሶምሶን ኀበ እግዚአብሔር ወይቤ፣ እግዚኦ እግዚኦ ተዘከረኒ ወአጽንዐኒ አሐተ እንከ እትቤቀል በቀለ አሐተ ህየንተ ክልኤሆን አዕይንቲየ እምነ ኢሎፍሊ ።

፴ ወአኀዘ ሶምሶን ለእልክቱ ክልኤሆን አዕማድ እለ ማእከል እለ ዲቤሆን ይቀውም ውእቱ ቤት ወገፍዖን አሐተ በየማኑ ወአሐተ በፀጋሙ ።

፴፩ ወይቤ ሶምሶን ለትሙት ነፍስየ ምስለ ሰብአ ኢሎፍሊ፣ ወአጠቆን በኀይሉ ወወድቀ ውእቱ ቤት ላዕለ መሳፍንተ ኢሎፍሊ ወላዕለ ኵሉ ሕዝብ ዘውስቴቱ፣ ወኮኑ እለ ሞቱ እለ ቀተለ ሶምሶን በሞቱ ፈድፋደ፣ እምእለ ቀተለ በሕይወቱ ።

፴፪ ወወረዱ አኀዊሁ ወኵሉ ቤተ አቡሁ ወዐርጉ ወነሥእዎ ወቀበርዎ ማእከለ ሦራሕ ወማእከለ ኤስታዎስ ውስተ መቃብረ ማኑሄ አቡሁ፣ ወኰነኖሙ ለእስራኤል ውእቱ ዕሥራ ዓመተ ።

ደሊላም በልቡ ያለውን ሁሉ እንደነገራት አውቃ፣ በልቡ ያለውን ሁሉ ነግሮኛልና አንድ ጊዜ ኑ ብላ የኢሎፍሊን አለቆች ልካ አስጠራቻቸው የኢሎፍሊም አለቆች ሁሉ ወደሷ መጡ፣ ከነሳቸውም ጋር ወርቅን አመጡ። መሳፍ፡ ፲፫ ፭፡ ፲፮ ፭፡

እሷም በጉልበቶቿ መካከል አስተኛችው፣ ጠጉር የሚቈርጥ ሰውን ጠርታ ሰባቱን የራሱን ብርንጐዎች አስቈረጠቻቸው፣ እሱም ይደክም ጀመር፣ ኃይሉም ተነሣው ።

ደሊላ ሶምሶንን ኢሎፍላውያን መጡብህ፣ አለችው፣ ከእንቅልፉም ተነሥቶ ወጥቼ እንደ ወትሮ አደርጋለሁ፣ አጠፋቸውም አለሁ ቢል እንደ ወትሮው ማድረግ ተሳነው እሱ ግን እግዚአብሔር እንደ ተለየው አላወቀም ።

ኢሎፍላውያንም ይዘው ሁለት ዓይኖቹን አወጧቸው ወደ ጋዛንም አውርደው በእግር ብረት አሰሩት በግዞትም ሆኖ እኽልን ይፈጭ ነበር ። ዘኁ፡ ፲፮ ፲፱ ።

ጠጉሩም ከላጩት በኋላ፣ ይበቅል (ያድግ) ጀመር ።

የኢሎፍሊም አለቆች ለጣኦታቸው መሥዋዕትን ይሠዉ ዘንድ ደስም ይላቸው ዘንድ ተሰበሰቡ፣ ፈጣሪያችን ጠላታችን ሶምሶንን በእጃችን ጣለልን አሉ ።

ሕዝቡም በዩት ጊዜ ፈጣሪያቸውን(ጣኦታቸውን) አመሰገኑት፣ አገራችንን ያጠፋት ሬሳዎቻችንንም ያበዛ ጠላታችንን በእጃችን ጣለው አሉ ። ዳን፡ ፭ ፬ ።

ከዚህ በኋላ በልተው ጠጥተው ደስ ባላቸው ጊዜ በፊታችን ይጫወት ዘንድ ሶምሶንን ከግዞት ቤት ጥሩት አሉ፣ ሶምሶንንም ከግዞት ቤት ጠርተዉት በሱ ተዘባበቱበት በሁለት ምሰሶዎች መካከልም አቆሙት ።

ሶምሶን ያን የሚመራውን ብላቴና አሳርፈኝ ይህ ቤት የቆመባቸው ምሰሶዎችንም አስጨብጠኝ ወደነሳቸውም አስጠጋኝ አለው፣ ያም የሚመራው ብላቴና እንዳለው አደረገለት ።

በዚያች ቤት ወንዶችም ሴቶችም መልተው ነበር፣ የኢሎፍሊ ሹማምንትም ሁሉ በዚያ በሰገነት ነበሩ፣ ሶምሶንም ሲጫወት ያዩት ዘንድ የተሰበሰቡ ወንዶችም ሴቶችም ሦስት ሺሕ ይሆኑ ነበር ።

ሶምሶንም ወደ እግዚአብሔር ጮኸ፣ አቤቱ! አቤቱ! አስበኝ እንዲቱ ነገርንም አድምጠኝ፣ እንግዲህ ስለ ሁለቱ ዓይኖቼ ፈንታ ከኢሎፍላውያን አንዲት በቀል ልመልስ አለ።

ሶምሶን ያ ቤት በላያቸው የተደገፈባቸው በመካከል ያሉ እነዚያን ሁለት ምሰሶች ያዛቸው አንዲቱን በቀኙ አንዲቱን በግራው፣ ይዞ ገፋቸው ።

ሶምሶን ሰውነቴ ከኢሎፍሊ ሰዎች ጋራ ትሙት ብሎ በኃይሉ ነቀነቃቸው፣ ያም ቤት በውስጡ ባሉ በሕዝቡ ላይና በኢሎፍሊ ሹማምንት ላይ ወደቀባቸው፣ የሞቱትም እንዲህ ሆኑ፣ ሶምሶን በሕይወቱ ሳለ ከገደላቸው ሲሞት የገደላቸው በዙ ።

ያባቱ ወገኖች ሁሉና ወንድሞቹም ወርደው ይዘው ወሰዱት በኤስታዎስ መከከልና በሦራሕ መከከል ባለ በአባቱ በማኑሄ መቃብር ቀበሩት፣ እሱም እስራኤልን ሃያ ዘመን ገዛቸው ። ኢያ፡ ፲፭ ፴፫ ። መሳ፡ ፲፫ ፳፭ ።

## ምዕራፍ ፲፯ ።

| | | |
|---|---|---|
| ወሀለወ ብእሲ ዘእምደብረ ኤፍሬም ዘስሙ ሚካ ። | ፩ | በኤፍሬም ነገድ ዕጣ ስሙ ሚካ የሚባል አንድ ሰው ነበር ። |
| ወይቤላ ሚካ ለእሙ ፣ ዝክቱ ወርቅ ዘትቤልኒ ተሰርቀኒ ወአምሐልኪ ናሁ ወርቁ ኀቤየ ውእቱ አነ ነሣእክዎ ፣ ወትቤ እሙ ቡሩክ ወልድየ ለእግዚአብሔር ። | ፪ | ሚካ እናቱን ተሰረቀብኝ ያልሽኝ ያማልሽበት ያ ብር እነሆ ብሩ በእኔ ዘንድ አለ ፣ እኔ ወስጄዋለሁ አላት ፣ እናቱም ልጄ ለእግዚአብሔር የተባረክህ ሁን አለችው ። |
| ወአግብአ ውእተ ወርቀ ዐሥርተ ወአሐደ ምእተ ለእሙ ፣ ወትቤ እሙ ቀድሶ ቀደስክዎ ለውእቱ ወርቅ ለእግዚአብሔር እምእዴየ ለባሕቲትየ ከመ ይትገበር ግልፎ ወስብክ ወይእዜኒ አገብአ ለከ ወእሁበከ ። | ፫ | ያንን ሺሕ መቶውን ወቄት ብር ለናቱ መለሰ ፣ እናቱም ያንን ብር መልክ ያለው ጣኦት ይሠራ ዘንድ ለእግዚአብሔር ከእጄ ብቻዬን ለየሁት ፣ አሁንም መልሼ እሰጥሃለሁ አላት ። ዘፀ፣ ፳ ፬ ። ዘሌ፣ ፲፱ ፬ ። |
| ወወሀበ ውእተ ወርቀ ለእሙ ወነሥአት እሙ ውእተ ወርቀ ወወሀበት እምኔሁ ክልኤተ ምእተ ብሩረ ለዘይሰብክ ወይገብር ግልፎ ወስብክ ፣ ወአንበርዎ ውስተ ቤተ ሚካ ። | ፬ | ያንንም ወርቅ ለናቱ ሰጣት ፣ እናቱም ያንን ብር ተቀብላ ከሱ ሁለት መቶውን ብር መልክ ያለው ጣኦት ለሚሠራው ሰው ሰጠችው ፣ በሚካ ቤትም አኖሩት ። |
| ወለብእሲሁሰ ሚካ ሎቱ ቤተ አማልክት ወገብረ ምስለ ወተራጺነ ወመልአ እዴሁ ለአሐዱ እምደቂቁ ወኮኖ ካህነ ። | ፭ | ለሚካም የጣኦታት ቤት ነበረው ፣ ምስልንም ሠራ ፣ የጣኦቱንም ልብስ አሠራ ፣ ከልጆቹም ያንዱን እጅ ቀብ ካህንም ሆነው ። ዘፍ፣ ፴፩ ፲፱ ። ዘፀ፣ ፳፱ ፱ ። |
| ወበእማንቱ መዋዕል አልቦሙ ንጉሥ ለደቂቀ እስራኤል ፣ ብእሲ ብእሲ ዘአደሞ ቅድመ አዕይንቲሁ ይገብር ። | ፮ | በነዚያም ወራቶች ለእስራኤል ልጆች ንጉሥ አልነበራቸውም ፣ አንዱም አንዱም ሰው በፊቱ መልካም መስሎ የታየውን ያደርግ ነበር ። መሳ፣ ፲፪ ፲ ። |
| ወሀለወ ወልድ ዘእምቤተልሔም ዘእምሕዝበ ይሁዳ ወእምዘመደ ይሁዳ ወሌዋዊ ውእቱ ብእሲሁ ወይነብር ህየ ። | ፯ | የይሁዳ ነገድ ዕጣ ከምትሆን ከቤተ ልሔም የተወለደ ከይሁዳ ወገን የሚሆን አንድ ሰው ነበረ ፣ ሰውየውም ካህን ነበር ፣ በዚያም ይኖር ነበር ። መሳ፣ ፲፱ ፩ ። |
| ወሖረ ውእቱ ብእሲ እምሀገረ ይሁዳ ወእምቤተ ልሔም ከመ ይኅድር ኀበ ረከበ ወበጽሐ ውስተ ደብረ ኤፍሬም ኀበ ቤተ ሚካ ከመ ይቢት ። | ፰ | ያም ሰው የሚኖርበትን ስፍራ ለመሻት ከቤተ ልሔምና ይሁዳ ከሚባል አገር ሂዶ ወደ ኤፍሬም ተራራ ደርሶ በዚያ ያድር ዘንድ ወደ ሚካ ቤት ገባ ። |
| ወይቤሎ ሚካ እምአይቴ መጻእከ ፣ ወይቤሎ ሌዋዊ አነ እምቤተ ልሔም ዘይሁዳ ወአሐውር እንበር ኀበ ረከብኩ ። | ፱ | ሚካም ከወዴት መጣህ ፣ አለው ፣ ያም ካህን እኔ የይሁዳ ዕጣ ከምትሆን ከቤተ ልሔም የመጣሁ ነኝ ፣ ባገኘሁበት አድር ዘንድ እሄዳለሁ አለው ። መሳ፣ ፲፩ ፵ ። |
| ወይቤሎ ሚካ ንበር ምስሌየ ወኩነኒ አበ ወካህነ ወአነ እሁበከ ዐሥሩ ኅብስተ ለለዕለትከ ወዘውገ አልባስ ወሲሳየከ ። | ፲ | ሚካም ከኔ ጋር ተቀመጥ አባትም ካህንም ሁነኝ አለው ፣ እኔም ዕለት ዕለት ዓሥር እንጀራ አፈራርቀህ የምትለብሰው ልብስንና ምግብህንም እሰጥሃለሁ አለው ። |
| ወአኀዘ ውእቱ ሌዋዊ ይንበር ምስለ ውእቱ ብእሲ ፣ ወኮኖ ውእቱ ወልድ ከመ አሐዱ እምደቂቁ ። | ፲፩ | ያም ካህን ከዚያ ሰው ጋራ ይኖር ዘንድ ጀመረ ፣ ያም ልጅ ከልጆቹ እንዳንዱ ሆነው ። ዘፀ፣ ፪ ፳፩ ። |
| ወመልአ እዴሁ ሚካ ለውእቱ ሌዋዊ ወኮኖ ውእቱ ወልድ ካህነ ወነበረ ውስተ ቤተ ሚካ ። | ፲፪ | ሚካም ያንን ካህን እጁን ቀባው ፣ ያም ልጅ ካህን ሆነው በሚካም ቤት ኖረ ። መሳ፣ ፲፯ ፭ ፣ ፲፰ ፴ ። |
| ወይቤ ሚካ ይእዜ አእመርኩ ከመ አሠነየ ላዕሌየ ገቢረ እግዚአብሔር እስመ ኮነኒ ሌዋዊ ካህነ ። | ፲፫ | ሚካ ሌዋዊ ካህን ሆኖልኛልና ፣ እግዚአብሔር በጎ ነገር እንዳደረገልኝ አሁን ዓወቅሁ አለ ። |

## ምዕራፍ ፲፰ ።

| | | |
|---|---|---|
| ወበእማንቱ መዋዕል አልቦሙ ንጉሥ ለእስራኤል ወበእማንቱ መዋዕል የኀሥሡ ሎሙ ርስተ ሰብአ ዳን ኀበ ይነብሩ እስመ ኢረከቡ እስከ ይእቲ አሚር ርስተ በማእከለ እስራኤል ። | ፩ | በነዚያ ወራቶች ለእስራኤል ንጉሥ አልነበራቸውም በነዚያም ወራቶች እስከ ዚያች ቀን በእስራኤል መካከል ርስት አላገኙም ነበርና ፣ የዳን ሰዎች የሚኖሩበትን ርስት ይፈልጉ ነበር ። መሳ፣ ፲፯ ፮ ፣ ፩ ፴፬ ። ኢያ፣ ፲፱ ፵፯ ። |
| ወፈነዉ ደቂቀ ዳን እምሕዝቦሙ ኀምስተ እደወ እመክፈልቶሙ ደቂቀ ኀይል እምነ ሦራኅ ወእስታሐል ከመ ይርአይዋ ለምድር ወያእምርዋ ፣ ወይቤልዎሙ ሑሩ ወርእዩ ለነ ምድረ ወበጽሑ ውስተ ምድረ ኤፍሬም ኀበ ቤተ ሚካ ፣ ወኀደሩ ህየ እሙንቱ ኀበ ቤተ ሚካ ። | ፪ | የዳንም ልጆች ከወገኖቻቸው ያችን አገር ያዩዋትና ያውቋት ዘንድ ከክፍላቸው ከእስታሐልና ከሦራሕ ሂዳችሁ ያችን አገር እዩልን ብለው ጽኑዓን የሆኑ አምስት ሰዎችን ላኩ ፣ እነዚያም ወደ ደብረ ኤፍሬም ደርሰው ወደ ሚካ ቤት ገቡ ፣ እነሳቸውም በዚያ በሚካ ቤት አደሩ ። |

፫ ወአእመርዎ ለውእቱ ወልድ ወሬዛ ሌዋዊ ወቦኡ ህየ ወይቤልዎ መኑ አምጽአከ ዝየ ወምንተ ትገብር በዝየ ወምንት ብከ በዝየ ።

ያን ካህን የሆነውን ሌዋዊ ልጅ ዐወቁት፣ ወደዚያውም ገብተው ወደዚህ ማን አመጣህ፤ በዚህ ምን ታደርጋለህ፤ በዚህስ ምን አለህ፤ አሉት ።

፬ ወይቤሎሙ ከመዝ ወከመዝ ረሰየኒ ሚካ ወዐሰበኒ ወኮንክዎ ካህነ ።

ሚክ እንዲህ እንዲህ አድርጎ ገዛኝ ቀጠረኝም ካህንም ሆንኩት አላቸው ። መሳ፣ ፲፯ ፲ ።

፭ ወይቤልዎ ተሰአል ለነ ኀበ እግዚአብሔር እመ ይሴርሕ ፍኖተነ እንተ ውስቴታ ነሐውር ንሕነ ።

እኛ የምንሄድበት ጐዳናችንን ያቀናልን እንደሁ፣ ወደ እግዚአብሔር አመልክትልን አሉት ።

፮ ወይቤሎሙ ውእቱ ካህን ሑሩ በሰላም ይእቲ ፍኖት ከሙ ቅድመ እግዚአብሔር እንተ ባቲ ተሐውሩ ።

ያም ካህን በእግዚአብሔር ፊት የምትሄዱበት ያችን ጐዳናችሁን በፍቅር አንድነት ሂዱ አላቸው ።

፯ ወሖሩ ኀምስቱ እደው ወበጽሑ ውስተ ሊሳ ወርእዩ ሕዝበ እለ ውስቴታ ተአሚኖሙ ይነብሩ በሕገ ሲዶና ህዱእነ ወዕሩፋነ እንዘ ይትአመኑ ወኢይክሉ ነቢበ ቃል ውስተ ምድረ ርስቱ መዝገበ ነገር እስመ ርኁቃን እሙንቱ እምነ ሲዶና ወአልቦሙ ትኅላፍ ምስለ ሶርያ ።

እነዚያም አምስት ሰዎች ሂደው ወደ ሊሳ ደረሱ፣ በሲዶና ሰዎች ሥራ አምነው ጸጥ ብለው የሚኖሩ ወገኖችንም አዩ፣ ከሲዶና የራቁ ነበሩና ከሶርያ ሰዎች ጋራ መተላለፊያ አልነበራቸውም ነበርና፣ በምድር ርስት ብዙ ነገርን መናገር አይችሉም ነበር ። መሳ፣ ፰ ፲፩ ።

፰ ወገብኡ እልክቱ ኀምስቱ እደው ኀበ አኀዊሆሙ ውስተ ሦራሕ ወአስታሐል ወይቤልዎሙ ምንተ ያነብረክሙ ።

እነዚያም አምስት ሰዎች ከወንድሞቻቸው ዘንድ ወደ አስታሐልና ወደ ሦራሕ ተመልሰው፣ ምን አስቀምጧችኋል፤ አሉዋቸው ።

፱ ተንሥኡ ንሑር ላዕሌሃ እስመ ቦአናሃ ወአንሶሰውናሃ ለይእቲ ምድር እስከ አጽናፊሃ፣ ወርኢነ ሕዝበ እለ ይነብሩ ውስቴታ በሕገ ሲዶና፣ ወርኁቃን እሙንቱ እምነ ሲዶና፣ ወአልቦሙ ትልኃፈ ነገር ምስለ ሶርያ ።

ገብተን በዚያች አገር እስከ ዳርቻዋ ድረስ ተመላልሰንበታልና፣ በሲዶና ሥርዓት ጸንተው በውስጧ የሚኖሩ ወገኖችንም አይተናልና እነሱቸውም ከሲዶና የራቁ ናቸውና ከሶርያም ሰዎች ጋራ በነገር መተዛዘን የላቸውምና ።

ያችን አገር እጅግ መልካም እንደሆነች አይተናታልና ተነሡ በነርሱ ላይ እንውጣ፣ እናንተ ግን ዝም በሉ ያችን አገር ትወርሷት ዘንድ ሂዶ መግባትን ቸል አትበሉ ።

፲ ወባሕቱ ተንሥኡ ወንዕርግ ላዕሌሆሙ እስመ ርኢናሃ ለይእቲ ምድር ሠናይት ጥቀ፤ ወአንትሙሰ አርምሙ ወኢትትሀከዩ ሐዊረ ወበዊአ ከመ ትትዋረስዋ ለይእቲ ምድር ።

ከገባችሁም በኋላ ተዘልለው ወደሚኖሩ ወገኖች ትደርሳላችሁ፣ አገሪቱም ሰፊ ናት፣ እግዚአብሔር በእጃችሁ አግብቶላችኋልና አገሪቱም በዚህ ዓለም ከተፈጠረው ነገር ሁሉ የሚታጣበት የለም አሏቸው ።

፲፩ ወእምከመ ቦእክሙ ትበጽሑ ኀበ ሕዝብ እለ ተአሚኖሙ ይነብሩ ወምድርኒ ረኃብ እስመ አግብአ እግዚአብሔር ውስተ እዴክሙ፤ ብሔር ዘአልቦ ዘይትኀጣእ እምኵሉ ቃል ዘተፈጥረ ውስተ ምድር ።

ከዚያ ከዳን አገር ከአስታሔልና ከሦራሕ ሰይፍ ሰይፍ የታጠቁ ስድስት መቶ ሰዎች መሣሪያቸውን ይዘው ተነሡ። መሳ፣ ፲፰ ፲፯ ።

፲፪ ወተንሥኡ እምህየ እምብሔረ ዳን እምነ ሦራሕ ወአስታሔል ስድስቱ ምእት ብእሲ እለ ቅኑታኒሆሙ ወይፀውሩ ንዋየ ሐቅሎሙ ።

ወጥተውም የይሁዳ ዕጣ በምትሆን በቀርያታርም ሰፈሩ፣ ስለዚህም ያ ቦታ እስከሁን ድረስ የዳን ሰፈር ተባለ ይኸውም ከቀርያታርም በኋላ ያለ ነው ። ኢያ፣ ፱ ፲፯ ።

፲፫ ወዐርጉ ወኀደሩ ውስተ ቀርያታርም ዘይሁዳ ወበእንተ ዝንቱ ተሰምየ ውእቱ መካን ትዕይንተ ዳን እስከ ዮም መንገለ ድኅሬሃ ለቀርያታርም ።

ከዚያም አልፈው ወደ ደብረ ኤፍሬም ደርሰው እስከ ሚክ ቤት ደረሱ ። መሳ፣ ፲፰ ፪ ። ፩ ሳሙ፣ ፲፬ ፲፰ ።

፲፬ ወኀለፉ እምህየ በጽሑ ውስተ ደብረ ኤፍሬም ወመጽኡ እስከ ኀበ ቤቱ ሚካ ።

፲፭ ወይቤልዎሙ እልክቱ ኀምስቱ እደው እለ ሖሩ ይርአይዋ ለይእቲ ምድረ ሊሳ ወይቤልዎሙ ለአኀዊሆሙ ሰበ ተአምሩ ከመ ቦቱ ውስተ ዝንቱ ቤት ምስል ወተራፊን ወግልፎ ወሰብክ ወይእዜኒ አእምሩ ዘትገብሩ ።

ሊሳ የምትባል ያችን አገር ያዩዋት ዘንድ የሄዱም እነዚያ አምስት ሰዎች ወንድሞቻቸውን በዚህ ቤት ምስል እንዳለ የጣአትም ልብስ እንዳለ ተመትቶ የተሠራ ጣአትም እንዳለ ብታውቁ ዝም ባላችሁም ነበር፣ አሁንም የምታደርጉትን ዕወቁ አሏቸው ። ዘፀ፣ ፳፫ ፩ ።

፲፮ ወተግኅሡ ህየ ወቦኡ ውስተ ቤቱ ለውእቱ ወልድ ሌዋዊ ውስተ ቤተ ሚካ ወተአምኅዎ ።

ከዚያም አልፍ ብለው በሚክ ቤት ወዳለ ካህን ወደ ሚሆን ወደዚያ ልጅ ቤት ገብተው እጅ ነሡት ።

፲፯ ወእልክቱ ስድስቱ ምእት ብእሲ እንዘ ይፀውሩ ንዋየ ሐቅሎሙ ቅኑታኒሆሙ ተጋብኡ ኀበ ኆኅተ አንቀጽ እለ እምደቂቀ ዳን ።

እሊያም ስድስት መቶ ሰዎች መሣሪያቸውን ይዘው አፋፋቸውን ታጥቀው ነበር፣ ከዳን ልጆች ወገን የሚሆኑ ሰዎች በበሩ ደጃፍ ተሰበሰቡ ። መሳ፣ ፲፰ ፲፩ ።

፲፰ ወዐርጉ እልክቱ ኀምስቱ እደው እለ ሖሩ ቀዲሙ ከመ ይርአዩ ምድረ ወቦኡ ወነሥኡ ዝክተ ምስለ ወግልፎ ወተራፊን ወሰብክ ወዝክቱሰ ካህን ይቀውም ኀበ ኆ

ያችን አገር ለማየት አስቀድመው ሂደው የነበሩ እነዚያ አምስቱ ሰዎችም ገቡ፣ ገብተውም መልክ ያለውን ጣኦትና ያንን ምስል ተመትቶ የተሠራውን ጣኦቱንና የጣ

ኅተ አንቀጽ ወእልክቱኒ ስድስቱ ምእት ብእሲ ይፀውሩ
ንዋየ ሐቅሎሙ ቅኑታኒሆሙ ።

፲፱ ወቦኡ እሙንቱ እደው ውስተ ቤተ ሚካ ወነሥኡ ዝ
ክተ ግልፎ ወምስለ ወተራፊን ወስብከ ወይቤሎሙ ዝክቱ
ካህን ምንተ ትገብሩ አንትሙ ።

፳ ወይቤልዎ አርምም ወደይ እዴከ ውስተ አፉከ ወነዓ
ምስሌነ ወትከውነነ አበ ወካህነ፤ ፀኑ ይኄይሰከ ትኩን ካ
ህነ ለአሐዱ ብእሲ እምትኩን ካህነ ለነገድ ወለሕዝበ እስ
ራኤል ።

፳፩ ወተፈሥሐ ልቡ ለውእቱ ካህን ወነሥአ ውእተ ምስለ
ወተራፊነ ወግልፎ ወስብከ ወቦአ ማእከለ ሕዝብ ።

፳፪ ወተመይጡ ወሖሩ ወነሥኡ ኵሎ ቤቶ ወጥሪቶ ወኵ
ሎ ክብሮ ወነድኡ ቅድሜሆሙ ።

፳፫ ወእንበለ ይርኅቁ እምቤት መጽአ ሚካ ወእደው ሕዝ
ብ እለ ቅድመ ቅሩበ ቤቱ ለሚካ ወጸርሑ እምድኅሬሆሙ
ለደቂቀ ዳን ወአውየዉ ሎሙ ለደቂቀ ዳን ።

፳፬ ወሚጡ ገጾሙ ደቂቀ ዳን ወይቤልዎ ለሚካ ምንተ
ኮንከ ዘትጸርሕ ።

፳፭ ወይቤሎሙ ሚካ ግልፎየኒ ዘገበርኩ ነሣእክሙኒ ወካ
ህነኒ ወሖርክሙ ወምንተ እንከ ኀደግሙ ሊተ ዘትብሉኒ
ምንተ ትጸርሕ ።

፳፮ ወይቤልዎ ደቂቀ ዳን ኢይሰማዕ እንከ ቃልከ ምስሌነ
ወእመ አኮሰ ይትራከቡከ እደው መሪራነ ነፍስ ወታሐጕል
ዓዲ ነፍስከኒ ወነፍሰ ቤትከኒ ።

፳፯ ወሖሩ ደቂቀ ዳን ፍናዊሆሙ ወርእየ ሚካ ከመ ይጸንዑ
ዕዎ ወተመይጠ ወአተወ ቤቶ ።

፳፰ ወእሙንቱሰ ነሥኡ ኵሎ ዘገብረ ሚካ ወካህነኒ ወኵ
ሎ ዘቦ ወሖሩ እስከ ሊሳ ላዕለ ሕዝብ ዘተአሚኖ ይነብር፤
ወቀተልዎሙ በአፈ ሐፂን ወሀገሮሙኒ አውዐዩ በእሳት ።

፳፱ ወአልቦ ዘድኅነ እስመ ርኁቃን እሙንቱ እምነ ሲዶና
ወአልቦሙ ትልሐፍ ምስለ ባዕድ ሰብእ ወይእቲሰ ውስተ
ቈላት እንተ ቤተ ጦብ፤ ወሐነጽዋ ለይእቲ ሀገር ወነበሩ
ውስቴታ ።

፴ ወሰመዩ ስማ ለይእቲ ሀገር ዳን በስመ አቡሆሙ ዳን ዘተ
ወልደ ለእስራኤል፤ ወስማሰ ለይእቲ ሀገር ቀዲሙ ሊሳ ።

፴፩ ወአቀሙ ሎሙ ደቂቀ ዳን ግልፎ ዘሚካ፤ ወዮናታን
ወልደ ጌርሶም ወልደ ሙሴ ውእቱ ወደቂቁ ካህናት እሙ
ንቱ ለሕዝበ ዳን እስከ አመ ፍልሰተ ምድሮሙ ።

፴፪ ወአቀሙ ሎሙ ግልፎ ዘሚካ ዘገብረ በኵሉ መዋዕል
አምጣነ ነበረ ቤተ እግዚአብሔር ውስተ ሴሎም፤ ወበእማ
ንቱ መዋዕል አልቦሙ ንጉሥ ለእስራኤል ።

ምዕራፍ ፲፱ ።

፩ ወሀሎ አሐዱ ብእሲ ሌዋዊ ወይነብር ውስተ አሐዱ

አቴን ልብስ ወሰዱ፤ ያ ካህን ግን በደጃፉ ቆሞ ነበር፤ እነ
ዚያም ስድስት መቶ ሰዎች መሣሪያቸውን ይዘው ሾፋቸ
ውን ታጥቀው ነበር ። መሳ፡ ፱ ፲፬፤ ፲፯ ፭ ።
እነዚያም ሰዎች ወደ ሚካ ቤት ገብተው ምስሉንና
ያን መልክ ያለውን ጣኦት ተመትቶ የተሠራውን ጣኦትን
የጣኦቱን ልብስ ወሰዱ፤ ያም ካህን ምን ታደርጋላችሁ፤
አላቸው ።
ዝም በል አፍህን በእጅህ ያዝና ከኛ ጋራ ሂድ፤ አባት
ካህን ትሆነንናለህ፤ ለእስራኤል ወገንና ለብዙ ነገድ ካህን
ከመሆን በውኑ ላንድ ሰው ካህን መሆን ይሻላሃልን፤
አሉት ። መሳ፡ ፲፯ ፲፤ ኢዮ፡ ፳፩ ፭፤ ምሳ፡ ፴ ፴፪ ።
የዚያም ካህን ልቡ ደስ አለው፤ የጣኦቱን ልብስና
ያንን ምስል ተመትቶ የተሠራውን ጣኦትና መልክ ያለ
ውን ጣኦት ይዞ ከሕዝቡ መካከል ገባ ።
እነዚያም ተመልሰው ሄዱ፤ ጥቃቅኑን ገንዘቡና ጓዙን
ሁሉ ከብቱንም (ሃብቱን) ሁሉ ወስደው በፊታቸው ነዱ ።
ከቤቱም ሳይርቁ ሚካ መጣ፤ በሚካ ቤት አቅራቢያ
አንጻር ያሉ ወገኖች ሰዎችም መጡ፤ በዳን ልጆች በስተ
ኋላ ሁነውም ጮኹ፤ ለዳን ልጆችም ጮኹላቸው ።
የዳንም ልጆች ፊታቸውን መልሰው ሚካን የምት
ጮኸ ምን ሁነህ ነው፤ አሉት ። መሳ፡ ፲፰ ፳፪ ፯ ፴፬ ።
ሚካም የሠራሁት ጣኦቴንም ካህኑንም ይዛችሁብኝ
ሂዳችሁ ለኔ ምን ተዋችሁልኝ፤ ለምን ትጮኻለህ ትሉኛ
ላችሁን፤ አላቸው ። ዘፍ፡ ፴፩ ፴ ።
የዳንም ልጆች እንግዲህ ቃልህ በኛ ዘንድ አይሰማ፤
ይህስ ካልሆነ ቁጡቁጡ ሰዎች ይገናኙኻል፤ ዳግመኛ ሰው
ነትህንና የወገኖችህን ሰውነት ታጠፋለህ አሉት ።
የዳን ልጆችም ጕዳናቸውን ሄዱ፤ ሚካም እንደጸኑ
በት አይቶ ተመልሶ ወደ ቤቱ ገባ ።
እነዚያ ሰዎች ሚካ የሠራውን ሁሉ ካህኑንም ያለ ገን
ዘቡንም ሁሉ ይዘው እስከ ሊሳ ድረስ ተዘልሎ በሚኖር
ወገን ላይ ሄዱ፤ በጦርም አጠፉዋቸው አገራቸውንም
በእሳት አቃጠሉ ። ዘዳ፡ ፴፫ ፳፪ ። መሳ፡ ፲፰ ፯ ።
እነሳቸው ከሲዶና የራቁ ናቸውና፤ ከሌላም ሰው ጋር
መተዛዘን የላቸውምና የዳን የለም፤ ይህችም አገር በጦብ
ወገን ቈላ ያለች ናት፤ ያችንም አገር ቀጽረዋት በውስጧ
ኖሩ ። ኢያ፡ ፲፱ ፳፰ ። መሳ፡ ፲፰ ፯ ።
የዚያችንም አገር ስሟን ከእስራኤል በተወለደ በአባ
ታቸው በዳን ስም "ዳን" አሏት፤ ቀድሞ ግን የዚያች አ
ገር ስም ሊሳ ይባል ነበር ። ዘፍ፡ ፲፬ ፲፬ ።
የዳን ልጆች የሚካን ጣኦት አቆሙላቸው፤ የሙሴ
ልጅ የጌርሳም ልጅ ዮናታንም እርሱና ልጆቹ አገራቸው
እስኪጠፋ ድረስ ካህናት ነበሩ ። መሳ፡ ፲፫ ፩ ።
የእግዚአብሔር ቤት በሴሎም የኖረውን ያህል በዘ
መኑ ሁሉ የሠራውን የሚካን ጣኦት አቆሙላቸው፤ በዚ
ያም ወራቶች ለእስራኤል ንጉሥ አልነበራቸውም ።

ምዕራፍ ፲፱ ።

ከደብረ ኤፍሬም በአንድ ጕን የሚኖር አንድ ካህን

## ኦሪት ዘመሳፍንት፣ ምዕራፍ ፲፱ ።

ኀብር ዘደብረ ኤፍሬም ወነሥአ ሎቱ ውእቱ ብእሲ ብእሲተ
ዕቅብተ እምቤተ ልሔም ዘይሁዳ ።
፪ ወተመዐቶ ዕቅብቱ ወኀደገቶ ወአተወት ቤተ አቡሃ
ቤተ ልሔም ዘይሁዳ ወነበረት ህየ መዋዕለ አርባዕተ
ኢውራኀ ።
፫ ወተንሥአ ምታ ወሖረ ወተለዋ ከመ ይትዓረቃ ወያ
ግብአ ኀቤሁ፣ ወቍልዔሁ ምስሌሁ ወክልኤቱ አእዱግ
ወሖረ ቤተ አቡሃ ወርእዮ አቡሃ ለይእቲ ወለት ወሖረ
ወተቀበሎ ።
፬ ወአብኦ ውስተ ቤቱ ወነበረ ምስሌሁ ሠሉሰ መዋዕለ
ወበልዑ ወሰትዩ ወቤተ ህየ ።
፭ ወአምዝ አመ ራብዕት ዕለት ነቅሐ በጽባሕ ወተንሥአ
ይሑር፣ ወይቤሎ አቡሃ ለይእቲ ወለት ለሐሙሁ አጽንዕ
ልበከ ወብላዕ ፍተ ኅብስት ወእምዝ ተሐውሩ ።
፮ ወነበሩ ወበልዑ ክልኤሆሙ ኅቡረ ወሰትዩ፣ ወይቤሎ
አቡሃ ለይእቲ ወለት ለውእቱ ብእሲ ቢት ዮምኒ ወይትፈ
ሣሕከ ልብከ ።
፯ ወተንሥአ ውእቱ ብእሲ ይሑር ወአገበሮ ሐሙሁ
ወከዐበ ቤተ ህየ ።
፰ ወነቅሐ በጽባሕ አመ ኃምስ ዕለት ከመ ይሑር ወይቤሎ
ሐሙሁ አቡሃ ለይእቲ ወለት ብላዕ እክለ ወእም ዝ ተሐውር
እስከ የዐርብ ፀሐይ ወበልዑ ወሰትዩ ክልኤሆሙ ።
፱ ወተንሥአ ውእቱ ብእሲ ከመ ይሑር ውእቱ ወዕቅ
ብቱ ወቍልዔሁ ምስሌሁ ወይቤሎ ሐሙሁ አቡሃ ለይእቲ
ወለት ናሁ መስየ ወተቈልቈለ ፀሐይ፣ ኅድር ዝየ ዮምኒ
ወንበር ዝየ ወይትፈሣሕከ ልብከ ወትገይሡ በጽባሕ ፍኖተ
ክሙ ወተአቱ ቤተከ ።
፲ ወአበየ ውእቱ ብእሲ በይተ ወተንሥአ ወሖረ ወበጽሐ
እስከ ቅድመ ኢያቡሴዎን እንተ ይእቲ ኢየሩሳሌም ወም
ስሌሁ ክልኤቱ አእዱግ ጽዑናን ወይእቲ ዕቅብቱ ምስሌሁ ።

፲፩ ወአንዘ ዓዲሆሙ ሀለዉ አንጻረ ኢያቡሴዎን ፀሐይኒ
ተቈልቈለት ጥቀ ወይቤሎ ቍልዔሁ ለእግዚኡ ነዓ ንግ
ኃሥ ውስተ ሀገረ ኢየሩሳሌም ዛቲ ወንቢት ውስቴታ ።
፲፪ ወይቤሎ እግዚኡ ኢይግኅሥ ውስተ ሀገረ ነኪር እን
ተ ኢኮነት ዘደቂቀ እስራኤል፣ ንኅልፍ እስከ ገባኦን ።
፲፫ ወይቤሎ እግዚኡ ለቍልዔሁ ነዓ ንግኃሥ ውስተ አ
ሐዱ መካን ወንኅድር ውስተ ገባኦን እንተ ስማ ራማ ።
፲፬ ወኀለፉ ወሖሩ እስከ ዐርበ ፀሐይ ወበጺሖሙ ገባኦን
እንተ ብንያም ግኅሡ በህየ ከመ ይባኡ ወይኅድሩ ውስተ
ገባኦን ።
፲፭ ወሰበ ቦኡ ወነበሩ ውስተ መርኅበ ሀገር አልበ ዘያበው
አሙ ውስተ ቤት ወዘያኅድሮሙ ።
፲፮ ወመጽአ ብእሲ ልሂቅ እምግብሩ ወብእሲሁሰ እምደ
ብረ ኤፍሬም ወምንባሪሁ ውስተ ገባኦን ወሰብአ ብሔርሰ
ደቂቀ ብንያም ።
፲፯ ወነፀሩ በአዕይንቲሆሙ ወርእይዎ ለዝክቱ ብእሲ ነጋ
ዲ ውስተ መርኅበ ሀገር ወይቤሎ ዝክቱ ልሂቅ አይቴ
ተሐውር ወእምአይቴ መጻእከ ።

ሰው ነበረ፣ ያም ሰው የይሁዳ ዕጣ ከምትሆን ከቤተ ል
ሔም አንዲት ሴት አግብቶ ይኖር ነበር ።
ሚስቱም ተጣላችው፣ ትታውም የይሁዳ ዕጣ በምት
ሆን በቤተ ልሔም ወደ አባቷ ሄደች፣ በዚያም አራት
ወር ተቀመጠች ። መሳ፣ ፲፩ ፹፣ ፲፮ ፩ ።
በኋላም ቍጣዋ ተከትሏት፣ ታርቆ ወደሱ ይመልሳት
ዘንድ ሄደ፣ ብላቴናውም ከሱ ጋራ ሂዶ ነበር፣ ሁለት አህ
ዮችም ጭነው ነበር፣ ወደዚያች ልጅ አባት ቤትም ሄደ፣
የዚያች ልጅ አባትም አየው፣ ሂዶም ተቀበለው ።
ወደ ቤቱም አግብቶት ከሱ ጋራ ሦስት ቀን ተቀመጠ፣
በልተውና ጠጥተውም በዚያ አደረ ።
ከዚህ በኋላ በአራተኛይቱ ቀን ማለዳ ነቅቶ ለመሄድ
ተነሣ፣ የዚያችም ልጅ አባት አማቹን ልቡናህን አጽን
ተህ እምበሽህን ብላ ከዚህ በኋላ ትሄዳላችሁ አለው ።
ሁለቱም አንድነት ተቀምጠው በሉ ጠጡ፣ የዚያች
ልጅ አባትም ያንን ሰው ዛሬም እደር ልብህንም ደስ ይበ
ለው አለው ። መሳ፣ ፲፱ ፳፪፣ ፪ ሳሙ፣ ፲፫ ፳፰ ።
ያም ሰው ለመሄድ ተነሣ፣ አማቹ ግድ አለው፣ ዳግ
መኛም በዚያ አደረ ።
በአምስተኛውም ቀን ይሄድ ዘንድ ማልዶ ተነሣ፣ የዚ
ያች ልጅ አባትም አማቹን እኽል ብላ፣ ከዚያ በኋላ ፀሐይ
እስኪገባ ድረስ ትሄዳለህ አለው፣ ሁለቱም በሉ ጠጡ ።
ያም ሰው ከሚስቱ ጋር ይሄድ ተነሣ፣ ብላቴናውም
ከሱ ጋር ሊሄድ ተነሣ፣ የዚያችም ልጅ አባት አማቱን
እነሆ መሸ፣ ፀሐይም ሊገባ ደረሰ፣ ዛሬም ከዚህ እደር
ከዚህም ተቀመጥ፣ ልብህም ደስ ይበለው ሲነጋ ጕዳናች
ሁን ትሄዳላችሁ ወደ ቤትህም ትገባለህ አለው ።
ያም ሰው አላደር ብሎ ተነሥቶ ሄደ፣ እስከ ኢያቡሴ
ዎን አፋዛገገም ደረሱ ይችውም ኢየሩሳሌም ናት፣ ከሱ
ም ጋር ሁለት የተጫኑ አህዮች ነበሩ፣ ያችም ሚስቱ
ከሱ ጋራ ነበረች ። ኢያ፣ ፲፭ ፷፫ ።
ገና በኢያቡሴዎን አንጻር ሳሉ ፀሐይ ፈጽሞ ሊገባ
ደርሶ ነበር፣ ብላቴናውም ጌታውን ገና ወደዚች ወደ ኢየ
ሩሳሌም እንግባ በዚም እንደር አለው ።
ጌታውም የእስራኤል ዕጣ ወዳልሆነች ወደ ባዕድ መን
ደር አልገባም፣ ወደ ገባኦን እንለፍ አለው ።
ጌታውም ወደ አንድ ቦታ ገብተን በገባዖን ስሟ
ራማ ከምትባል መንደር እንደር አለው ።
ፀሐይ እስኪገባ ድረስ አልፈው ሄዱ፣ የብንያም ዕፃ
ወደ ምትሆን ወደ ገባዖንም በደረሱ ጊዜ ገብተው በገባ
ዖን ያድሩ ዘንድ ወደዚያ አቀኑ ።
ገብተውም ከአገሩ አደባባይ በተቀመጡ ጊዜ፣ ወደ
ቤት አግብቶ የሚያሳድራቸው አላገኙም ። መሳ፣ ፲፱ ፲፰ ።
ሽማግሌ ሰው ከሥራው መጣ፣ ሰውዬው ግን በደብረ
ኤፍሬም ነበር፣ የሚኖረውም በገባዖን ነበር፣ የዚያ አገር
ሰዎች ግን የብንያም ልጆች ነበሩ ።
በዓይናቸውም ተመልክተው ያንን አልፎ ሃያጅ ሰው
በአገሩ አደባባይ አዩት፣ ያም ሽማግሌ ሰው ወዴት ትሄዳ
ለህ፣ ከየትስ መጣህ፣ አለው ።

፲፰ ወይቤሉ ኀለፍት ንሕነ እምቤተ ልሔም ዘይሁዳ እስከ አመ ንበጽሕ ደብረ ኤፍሬም እስመ እምህየ አነ ወሖርኩ እስከ ቤተ ልሔም ዘይሁዳ ወአአቱ ቤትየ ወአልቦ ዘአግኀሠኒ ውስተ ቤቱ ።

፲፱ ወኀሠርኒ ወእክልኒ ብነ ለአእዱጊነ ወኅብስትኒ ወወይንኒ ብነ ለአመትክኒ ወለገብርከኒ ወለቍልዔከኒ አልቦ ዘነኀጥአ እምኵሉ መፍቅድነ ።

፳ ወይቤሎ ዝክቱ ብእሲ ልሂቅ ሰላም ለከ ወኵሉ ዘአልብከ ላዕሌየ ወባሕቱ ውስተ መርኅብስ ኢትኅድር ።

፳፩ ወአብኦ ውስተ ቤቱ ወአቅምሐ ለአእዱጊሁ ወሐፀበሙ እገሪሆሙ ወበልዑ ወሰትዩ ።

፳፪ ወእምዝ ሰበ ተፈሥሑ ልቦሙ ናሁ ደቂቀ ኃጥአን ሰብአ ሀገር ዐገትዎ ለውእቱ ቤት ወጐድጐዱ ኆኅቶ ወይቤልዎ ለዝክቱ ብእሲ ልሂቅ በዓለ ቤት አውፅኦ ለዝክቱ ብእሲ ዘቦአ ውስተ ቤትከ ከመ ንሑሮ ።

፳፫ ወወፅአ ኀቤሆሙ ዝክቱ ብእሲ በዓለ ቤት ወይቤሎሙ ሐሰ ለክሙ አኀዊነ ኢትግበሩ እኩየ እምድኅረ ቦአ ብእሲ ውስተ ቤትየ ኢትግበሩ ዘንተ ዕበደ ።

፳፬ ናሁ ወለትየ ድንግል ወዕቅብቱ ወአውፅኦን ወአኅሥርዎን ወግበሩ ላዕሌሆን ዘይኤድመክሙ በውስተ አዕይንቲክሙ ወላዕለ ዝክቱስ ብእሲ ኢትግበሩ ዘንተ ነገረ ዕበድ ።

፳፭ ወኢፈቀዱ እሙንቱ ሰብእ ይስምዕዎ ፣ ወነሥኦ ዝክቱ ብእሲ ለዕቅብቱ ወአውፅኦ አፍኣ ኀቤሆሙ ወአኀሠርዋ ወተዋነይዋ ኵላ ሌሊተ እስከ ጸብሐ ወፈነውዋ ሰበ ሠርከ ኀሕ ።

፳፮ ወመጽአት ይእቲ ብእሲት በጽባሕ ወወድቀት ኀበ መድረከ ኆኅት ዘውእቱ ብእሲ በዓለ ቤት ኀበ ሀለወ ህየ እግዚኣ እስከ ጸብሐ ።

፳፯ ወተንሥአ እግዚኣ በጽባሕ ወአርኀወ ኆኅተ ውእቱ ቤት ወወፅአ ከመ ይሑር ፍኖቶ ወረከባ ለዕቅብቱ ውድቅተ ኀበ ኆኅተ ውእቱ ቤት ወእደዊሃ ላዕለ መድረክ ።

፳፰ ወይቤላ ተንሥኢ ንሑር ወኢያውሥአቶ እስመ ሞተት ፣ ወጸዐና ዲበ አድጉ ወተንሥአ ውእቱ ብእሲ ወአተወ ብሔሮ ።

፳፱ ወቦአ ቤቶ ወነሥአ መጥባሕተ ወአኀዞ ለዕቅብቱ ወመተራ እመለያልየ አዕፅምቲሃ ዐሠርተ ወክልኤተ ክፍለ ረሰያ ወፈነዋ ውስተ ሕዝበ እስራኤል ።

፴ ወእምዝ ኵሉ ዘርእያ ይቤ አልቦ አመ ኮነ ከመዝ ወአልቦ አመ አስተርአየ እምአመ ወፅኡ እስራኤል እምግብጽ እስከ ዮም ።

፴፩ ወአዘዞሙ ውእቱ ብእሲ ለእልክቱ ሰብእ እለ ፈነዎሙ ወይቤሎሙ ከመዝ በልዎሙ ለኵሉ ሰብአ እስራኤል ቦኑ አመ ኮነ ከመዝ እምአመ ወፅኡ ደቂቀ እስራኤል እምግብጽ እስከ ዮም ፣ ወረስዩ ለክሙ ምክረ ወተናገሩ ዘይሤኒ ።

ወደ ደብረ ኤፍሬም እስክንደርስ ድረስ የይሁዳ ዕጣ ከምትሆን ከቤተ ልሔም አልፈን የምንሄድ ነን፤ እኔም ከዚያ ነኝና የይሁዳ ዕጣ ወደምትሆን ወደ ቤተ ልሔም ሂጄ ነበር፤ አሁንም ወደ ቤቴ እመለሳለሁ፤ ወደ ቤቱም ያገባኝ የለም ።

ለአህዮቻችንም ገለባ (ገፈራ) አለን፤ ላገልጋይህ ለሚስቱም ለብላቴናህም ወይንና እምባሻ አለን፤ ከምንፈልገው ሁሉ የምናጣው የለም አለው ።

ያም ሽማግሌው ሰው ደስ ይበልህ፤ ላንተ የሌለህ ሁሉ ከኔ ዘንድ አለ፤ ነገር ግን በአደባባይ አትደር አለው ።

ወደ ቤቱም አገባው፤ ለአህዮቹም ገፈራ ጣለላቸው፤ እግራቸውንም አጠባቸው፤ በሉም ጠጡም ።

ከዚህ በኋላ በልተው ጠጥተው ልቡናቸውን ደስ ባለው ጊዜ እነሆ ኃጥአን የሚሆኑ የአገሩ ሰዎች ያንን ቤት ከበቡት፤ በሩንም ደበደቡ፤ ያነንም የቤቱ ባለ ቤት ሽማግሌ ሰው እንደርስበት ዘንድ ወደ ቤትህ የገባውን ያንን ሰው አውጣልን አሉት ። ዘፍ፡ ፲፱ ፭ ። ዘዳ፡ ፲፫ ፲፫ ።

ያም የቤቱ ጌታ ሰው ወደነሳቸው ወጥቶ ወንድሞቼ! ለናንተ አገባባችሁ አይደለም ሰውዬው ወደ ቤቴ ከገባ በኋላ ክፉ ነገር አታድርጉ፤ ይህን ስንፍና አትሥሩ ።

እነሆ ሚስቱና ከወንድ ያልደረሰች ልጄ አሉ፤ እነሱን ላምጣላችሁ አዋርዱዋቸው፤ በነሱ ላይ ለዓይናችሁ ደስ የሚያሰኛችሁን አድርጉ፤ በዚህ ሰው ግን ይህን የስንፍና ሥራ አታድርጉ አላቸው ። ዘፍ፡ ፲፯ ፯ ። ዘዳ፡ ፳፩ ፲፬ ።

እነዚያም ሰዎች ይሰሙት ዘንድ አልወደዱም፤ ያም ሰው ሚስቱን ይዞ ወደነሳቸው አወጣት፤ አዋረድዋት፤ እስኪነጋም ድረስ በፈረቃ ተጫወቱባት፤ ጎህ በቀደደ ጊዜም ለቀቋት ። ፩ ሳሙ፡ ፴፩ ፬ ።

ያችም ሴት ሲነጋ መጥታ በዚያ ባሏ ባለበት በቤቱ ጌታ ሰው ደጃፍ መድረክ ላይ እስኪነጋ ድረስ ወደቀች ። መዝ፡ ፵፯ ፩ ።

ባልዋ ማለዳ ተነሥቶ የዚያን ቤት ደጃፍ ከፈተ፤ ጐዳናውንም ይሄድ ዘንድ ቢወጣ ሚስቱን በዚያ ቤት ደጃፍ ወድቃ እጆቿን በመድረኩ ላይ ዘርግታ አገኛት ።

ተነሺ እንሂድ አላት፤ ሙታለችና አልመለሰችለትም በህያውም ላይ ጭናት ያ ሰው ወደ አገሩ ተመለሰ ። መሳ ፳ ፭ ።

ወደ ቤቱ ገብቶ ሰይፍን አምጥቶ ሚስቱንም ይዞ ከየአጥንቶቿ መለያያ ላይ ቈራርጦ ዓሥራ ሁለት ክፍል አደረጋት፤ ወደ እስራኤልም ወገኖች ሰደዳት ።

ከዚህ በኋላ ያያት ሁሉ እስራኤል ከግብጽ ከወጡ ጀምሮ እስከሁን ድረስ እንዲህ ያለ ነገር ተደርጎም ታይቶም አያውቅም አለ ።

ያም ሰው የላካቸውን እነዚያን ሰዎች የእስራኤልን ወገኖች ሁሉ እንዲህ በሏቸው፤ የእስራኤል ልጆች ከግብጽ ከወጡ ጀምሮ እስካሁን ድረስ በውኑ እንደዚህ ተደርጎ ያውቃልን፤ እናንተ ምክር አድርጉ የሚሆነውን ነገር ተነጋገሩ ብሎ አዘዛቸው ። መሳ፡ ፳ ፯ ። ኢሳ፡ ፰ ፲ ።

## ምዕራፍ ፳።

፩ ወወፅኡ ኵሎሙ ደቂቀ እስራኤል ወአንገለጉ ወተጋብኡ ኵሉ ማኅበሮሙ ከመ አሐዱ ብእሲ እምዳን እስከ ቤርሳቤሕ ወገለዓድኒ ውስተ መሴፋ።

፪ ወቆመ ኵሉ ሕዝብ ወኵሉ ነገደ እስራኤል ውስተ ማኅበሮሙ ወኵሉ ሕዝቡ ለእግዚአብሔር አርባዕ እልፍ እጋር ዘይጸውሩ ኲናተ።

፫ ወሰምዑ ደቂቀ ብንያም ከመ ተጋብኡ ደቂቀ እስራኤል ውስተ መሴፋ ወይቤሉ ደቂቀ እስራኤል አይድዑነ በአይቴ ኮነት ዛቲ እኪት።

፬ ወአውሥአ ዝኩ ካህን ሌዋዊ ምታ ለእንታክቲ ብእሲት እንተ ቀተሉ ወይቤ በገባአን ዘብንያም መጻእኩ አነ ወዕቅብትየ ንኅድር።

፭ ወተንሥኡ ላዕሌነ ሰብአ ገባአን ወዐገቱ ዲቤነ ውእተ ቤተ ሌሊተ ወኪያየ ፈቀዱ ይቅትሉኒ ወለዕቅብትየሰ አኅሠርዋ ወተዋነይዋ ወሞተት።

፮ ወነሣእክዋ ለዕቅብትየ ወመተርክዋ በበመለያልይ ወፈነውኩ ውስተ ኵሉ ደወለ ርስቶሙ ለእስራኤል እስመ ገብሩ ዕበደ ውስተ እስራኤል።

፯ ወናሁ ኵልክሙ አንትሙ ደቂቀ እስራኤል ዝየ አቅሙ ለክሙ ቃለ ወምክረ።

፰ ወቆሙ ኵሉ ሕዝብ ከመ አሐዱ ብእሲ ወይቤሉ ኢንአቱ አብያቲነ ወኢንገብእ በሐውርቲነ።

፱ ወይእዜኒ ከመዝ ግበሩ ላዕለ ገባአን ነዐርግ ላዕሌሆሙ በበመክፈልትነ።

፲ ወንነሥእ በበዐሠርቱ እደው ለምእት ለኵሉ ሕዝበ እስራኤል ወከማሁ ምእተ ለዐሠርቱ ምእት፡ ወዐሠርተ ምእተ ለእልፍ እለ ይፀውሩ ስንቀ ለሕዝብ ውስተ ፍኖት ለእለ የሐውሩ ይትቃተልዎሙ ለገባአን ዘብንያሚ በበይነ ኵሉ ዕበድ እንተ ገብሩ ላዕለ እስራኤል።

፲፩ ወተጋብኡ ኵሉ እስራኤል እምአህጉሪሆሙ፡ ወለአኩ ሕዝበ እስራኤል ውስተ ኵሉ ነገደ ብንያሚ እንዘ ይብሉ ምንት ዛቲ እኪት እንተ ኮነት በውስቴትክሙ።

፲፪ ወይእዜኒ አምጽኡ እደወ እለ አበሱ በገባአን ደቂቀ ዓመፃ ወንቅትሎሙ ወናወፅእ እኪተ እምደቂቀ እስራኤል ወአበዩ ደቂቀ ብንያሚ ሰሚዖቶሙ ለደቂቀ እስራኤል።

፲፫ ወተጋብኡ ደቂቀ ብንያሚ እምአህጉሪሆሙ ውስተ ገባአን ከመ ይፃኡ ይትቃተልዎሙ ለደቂቀ እስራኤል።

፲፬ ወተኈለቁ ደቂቀ ብንያሚ በይእቲ ዕለት እምአህጉሪሆሙ ክልኤቱ እልፍ ወኀምሳ ምእት ብእሲ እለ ያፀውሩ ኲናተ እንበለ እለ ይነብሩ ውስተ ገባአን።

፲፭ ወእሙንቱኒ ተኈለቁ ሰብዐቱ ምእት ወራዙት ኀሩያን እለ ክልኤሆን እደዊሆሙ የማናውያን ኵሎሙ ወኵሎሙ እሉ ወፃፍያን በሞፀፍት እብን ወየሀይጹ ሥዕርተ ወኢይስሕቱ።

፲፮ ወተኈለቁ ኵሎሙ ደቂቀ እስራኤል እንበለ ደቂቀ ብንያሚ አርባዕ እልፍ ብእሲ ዐዋሬ ኲናት ወኵሎሙ እሉ እደው መስተቃትላን።

## ምዕራፍ ፳።

፩ የእስራኤል ልጆች ሁሉ ወጥተው ተሰበሰቡ፡ ከዳን እስከ ቤርሳቤሕ በመሴፋ እስከለች እስከ ገለዓድም ድረስ ያሉ ወገኖቻቸው ሁሉ እንደ አንድ ሰው ሁነው ተሰበሰቡ።

፪ ሕዝቡ ሁሉ የእስራኤልም ነገድ ሁሉ በወገኖቻቸው በጠላትነት የተነሡ የእግዚአብሔርም ወገኖቹ ሁሉ ለጦር የደረሰው ተቈጥሮ አርባ እልፍ አርበኞች ናቸው።

፫ የብንያምም ልጆች የእስራኤል ልጆች በመሴፋ እንደ ተሰበሰቡ ሰሙ፤ የእስራኤልም ልጆች ይህች ክፉት የትም ቦታ እንደሆነች ንገሩን አሏቸው።

፬ የተገደለችው የዚያች ሴት ባል ከሌዊ የተወለደ ያ ካህንም የብንያም ዕፃ በምትሆን በገባአን ነው ብሎ መለሰ እኔም ከሚስቴ ጋራ እናድር ዘንድ መጣሁ። ዘዐ፡ ፪ ፲፬።

፭ የገባአንም ሰዎች ተነሥተው በኛ ላይ ያንን ቤት ከበቡት፤ እኔንም ይገድሉኝ ዘንድ ፈለጉ፤ ሚስቴን ግን አጐሳቈሏት፤ በፈረቃም ተጫወቱባት ሞተች።

፮ አምጥቼም በየአጥንቷ መለያያ ቈራረጥኋት በእስራኤል ዘንድ ስንፍናን አድርገዋልና በእስራኤል ርስት አውራጃ ሁሉ ሰደድኩ። መሳ፡ ፲፱ ፳፫-፳፱።

፯ እነሆ እናንተ የእስራኤል ልጆች ምክርንና ነገርን በዚህ ፈጽሙ። መሳ፡ ፲፱ ፴።

፰ ሕዝቡም ሁሉ እንደ አንድ ሰው ተነሥተው ወደ ቤታችን እንገባም፤ ወደ አገራችንም እንመለስም አሉ።

፱ አሁንም እንዲህ አድርጉ በየክፍላችን በገባአን ሰዎች ላይ እንዘምታለን። ኢያ፡ ፲፬ ፪። ፩ ሳሙ፡ ፩ ፳፩።

፲ በእስራኤል ላይ ስላደረጉት ስንፍና ሁሉ የብንያም ዕጣ የምትሆን የገባአንን ሰዎች ይዋጉዋቸው ዘንድ ለሚሄዱ ወገኖች በጐዳና ስንቅ የሚሸከሙ ሰዎችን ከእስራኤል ወገኖች ሁሉ በመቶው ዓሥር ዓሥር እንደዚሁም ለሺው መቶ መቶ ለእልፉም ሺሕ ሺሕ እንሰዳለን አሉ።

፲፩ እስራኤል ሁሉ ከአገሮቻቸው ተሰብስበው የእስራኤል ወገኖች ሁሉ በናንተ የተደረገች ይህች ክፉት ምንድር ናት፤ ብለው ወደ ብንያም ነገድ ሁሉ ላኩ።

፲፪ አሁንም በገባአን የበደሉ ሰዎችን እንግደላቸው፤ ከእስራኤል ልጆች ክፉትን እናውጣ አሏቸው፤ የብንያምም ልጆች የእስራኤልን ልጆች አንሰማችሁም አሏቸው።

፲፫ የብንያምም ልጆች የእስራኤልን ልጆች ወጥተው ይዋጉዋቸው ዘንድ ከአገሮቻቸው ወጥተው በገባአን ተሰበሰቡ።

፲፬ የብንያምም ልጆች ከአገሮቻቸው ተሰብስበው በዚያች ቀን ተቈጠሩ፤ በገባአን ከሚኖሩት በቀር ለጦር የደረሱት ሁለት እልፍ አምስት ሺሕ ናቸው። ዘኍ፡ ፩ ፴፯፣ ፳፮ ፵፩።

፲፭ እነዚያም የተመረጡ ሰባት መቶ አርበኞች ተቈጠሩ፤ ሁሉም በቀኛቸውና በግራቸው የሚወረውሩ ናቸው፤ እነዚህም ሁሉ በወንጭፍ ደንጊያ የሚወረውሩ የማይስቱ ከራስ ጠጕር ለይተው የሚመቱ ናቸው።

፲፮ ከብንያም ልጆች በቀር የእስራኤል ልጆች ሁሉ ተቈጥረው ለጦር የደረሱ አርባ እልፍ ሆኑ፤ እነዚያም ሁሉ አርበኞች ናቸው። ዘኍ፡ ፩ ፵፮፣ ፳፮ ፶፩።

| | | |
|---|---|---|
| ወተንሥኡ ወዐርጉ ውስተ ቤቴል ወተሰአሉ ኀበ እግዚአብሔር ወይቤሉ ደቂቀ እስራኤል መኑ የዐርግ ለነ መስፍነ ዘይትቃተሎሙ ለነ ለብንያሚ ወይቤሎሙ እግዚአብሔር ይሁዳ ይዕርግ ለክሙ መስፍነ ። | ፲፯ | ተነሥተውም ወደ ቤቴል መጡ፤ እግዚአብሔርንም ጠየቁ፤ የእስራኤል ልጆች የብንያምን ልጆች ወጥቶ የሚዋጋልን መስፍን ማን ነው፤ አሉ እግዚአብሔርም ይሁዳ መስፍን ሆኖ ይውጣላችሁ አላቸው ። ዘኁ፡ ፳፯ ፳፩ ። |
| ወተንሥኡ ደቂቀ እስራኤል ወኀደሩ ላዕለ ገባእን ። | ፲፰ | የእስራኤልም ልጆች ተነሥተው በገባእን ሰፈሩ ። |
| ወወፅኡ ኵሎሙ እደወ እስራኤል ውስተ ቀትል ምስለ ብንያሚ ወተአኀዝዎሙ በገባእን ። | ፲፱ | የእስራኤልም አርበኞች ሁሉ ከብንያም ልጆች ጋራ ለመዋጋት ወደ ሰልፍ ወጥተው በገባእን ተያያዙዋቸው (ተቈራቈሷቸው) ። |
| ወወፅኡ ደቂቀ ብንያሚ እምሀገር ወቀተሉ እምእስራኤል ክልኤተ እልፈ ወዕሥራ ምእተ ብእሴ ይእተ አሚረ እለ ወድቁ ውስተ ምድር ። | ፳ | የብንያምም ልጆች ከአገር ወጥተው ከእስራኤል ወገን ሁለት እልፍ ከሁለት ሺሕ ሰው ገደሉ፤ የዚያን ጊዜ ገደል ገብተው የሞቱ ብዙ ናቸው ። |
| ወተጸንዑ ደቂቀ እስራኤል ወዳግመ ወፅኡ ይትቃተሉ ውስተ ዝክቱ መካን ኀበ ተቃተሉ አመ ቀዳሚት ዕለት ሀየ ። | ፳፩ | የእስራኤልም ልጆች በዚያች ቀን ተጸናንተው በመጀመሪያው ቀን በዚያ ወደ ተዋጉበት ዳግመኛ ይዋጉ ዘንድ ወደዚያ ቦታ ወጡ ። |
| ወዐርጉ ደቂቀ እስራኤል ወበከዩ ቅድመ እግዚአብሔር እስከ ሠርክ ወተሰአሉ ኀበ እግዚአብሔር ወይቤሉ ንድግምኑ ዓዲ ተቃትሎ ምስለ ብንያሚ እኁነ፤ ወይቤሎሙ እግዚአብሔር ዕርጉ ኀቤሆሙ ። | ፳፪ | የእስራኤል ልጆች በእግዚአብሔር ፊት እስከ ሠርክ ድረስ አለቀሱ፤ ከወንድማችን ከብንያም ልጆች ጋራ ዳግመኛ እንዋጋለንን፤ ብለው እግዚአብሔርን ጠየቁ፤ እግዚአብሔርም ወደነሱ ውጡ አላቸው ። |
| ወመጽኡ ደቂቀ እስራኤል ኀበ ብንያሚ አመ ሣኒታ ዕለት ። | ፳፫ | የእስራኤልም ልጆች በሁለተኛው ቀን ወደ ብንያም ልጆች መጡ ። |
| ወወፅኡ ብንያሚ ወተቀበልዎሙ ወተቃተልዎሙ አመ ሣኒታ ዕለት እምገባእን ወቀተሉ እምኔሆሙ እልፈ ወሰማንያ ምእተ ብእሴ እለ ወድቁ ውስተ ምድር ወኵሎሙ እለ ይፀውሩ ኵናተ ። | ፳፬ | የብንያምም ልጆች ወጥተው ተቀበሏቸው፤ በማግሥቱም ዕለት በገባእን ተዋጉዋቸው ከነሱቸውም እልፍ ከስምንት ሺሕ ሰዎች ገደሉ፤ ገደል ወድቀው በሕር ጠልቀው የሞቱ ብዙ ናቸው፤ ሁሉም ለጦር የደረሱ ናቸው ። |
| ወዐርጉ ኵሎሙ ደቂቀ እስራኤል ወኵሉ ሕዝብ ወሖሩ ውስተ ቤቴል ወበከዩ ወነበሩ ሀየ ቅድመ እግዚአብሔር ወጾሙ ደቂቀ እስራኤል እስከ ሠርክ ወአዕረጉ መሥዋዕተ መድኀኒት ለእግዚአብሔር ። | ፳፭ | የእስራኤል ልጆች ሁሉ ወጡ፤ ሕዝቡም ሁሉ ወጥተው ወደ ቤቴል ሄደው አለቀሱ፤ በዚያም በእግዚአብሔር ፊት ተቀምጠው የእስራኤል ልጆች እስከ ሠርክ ድረስ ጾሙ፤ ድኅነት የሚያሰጥ መሥዋዕትንም ለእግዚአብሔር አቀረቡ ። መሳ፡ ፩ ፲፫ ። |
| ወተስእሉ ደቂቀ እስራኤል ኀበ እግዚአብሔር ወሀለወት ሀየ ታቦተ እግዚአብሔር በእማንቱ መዋዕል ። | ፳፮ | የእስራኤል ልጆች ወደ እግዚአብሔር ጠየቁ፤ በዚያ ወራት የእግዚአብሔር ማደሪያ (ታቦት) በዚያ ነበረች ። |
| ወፊንሐስ ወልደ አልአዛር ወልደ አሮን ይቀውም ቅድሜሃ በእማንቱ መዋዕል ወይቤሉ ንድግምኑ ዓዲ ወፂአ ውስተ ቀትል ምስለ ደቂቀ ብንያሚ እኁነ አው ንኅድግ ወይቤሎሙ እግዚአብሔር ዕርጉ እስመ ጌሠመ አገብአሙ ውስተ እዴክሙ ። | ፳፯ | የአሮን ልጅ የአልአዛር ልጅ ፊንሐስ በዚያ ወራት ከፊቷ ይቆም ነበር፤ ከወንድማችን ከብንያም ልጆች ጋራ ለመዋጋት አሁን ዳግመኛ እንውጣ ወይስ አንውጣ፤ አሉ፤ እግዚአብሔርም፤ ነገ በእጃችሁ እጥላቸዋለሁና ውጡ አላቸው ። ዘኁ፡ ፳፭ ፯ ። ዘዳ፡ ፲ ፰ ። |
| ወአንበሩ ደቂቀ እስራኤል እለ የዐግትዋ ለገባእን ዐውዳ ። | ፳፰ | የእስራኤም ልጆች ገባእንን ዙርያዋን የሚከቡዋትን ሰዎች አኖሩ ። ኢያ፡ ፫ ፬ ። |
| ወተአኀዝዎሙ ደቂቀ እስራኤል ለብንያሚ አመ ሣልስት ዕለት ወተቃተልዎሙ በኀበ ገባእን ከመ ቀዲሙ ። | ፳፱ | የእስራኤል ልጆች በሦስተኛይቱ ቀን የብንያሚን ልጆች ተያያዙዋቸው እንደቀደመውም በገባእን ይዋጉዋቸው ጀመር ። |
| ወወፅኡ ደቂቀ ብንያሚ ወተቀበልዎሙ ለሕዝብ ወጉዩ እምኀበ ሀገር ወአኀዙ ይትቃተሉ እምሕዝብ ከመ ቀዲሙ በውስተ ፍኖት አሐቲ እንተ ታዐርግ ለቤቴል ወአሐቲ እንተ ታዐርግ ለገባእን በውስተ ገዳም ወየአክሉ ሠላሳ እልፍ ብእሲ እምእስራኤል ። | ፴ | የብንያምም ልጆች ወጥተው ሕዝቡን ተቀበሏቸው፤ ከሀገሩም ሸሹ፤ ከሕዝቡም እንደቀደመው አንዲቱ ወደ ገባእን በምታወጣ አንዲቱ ወደ ቤቴል በምታወጣ ጎዳና ይዋጉ ጀመር፤ በምድረ በዳ ከእስራኤል ሠላሳ እልፍ የሚሆኑ ሰዎች ነበሩ ። መሳ፡ ፳ ፲፰፡ ፳፩ ፱፡ ፲፪ ፲፱ ። |
| ወይቤሉ ደቂቀ ብንያሚ ይመውቱ ቅድሜነ ከመ ቀዲሙ፤ ወይቤሉ ደቂቀ እስራኤል ንጕየይ ወናርኅቆሙ እምሀገር ውስተ ፍናዌ ። | ፴፩ | የብንያሚም ልጆች እንደቀደመው በፊታችን ይሞታሉ አሉ፤ የእስራኤልም ልጆች ሸሽተን ከከተማ ወደ ጎዳና እናርቃቸው አሉ ። ኢያ፡ ፰ ፫-፯ ። |

፴፫ ወተንሥኡ ኵሎሙ ሰብአ እስራኤል እምነ መካኖሙ ወተቃተሉ በበዓልታምር ፡ ወማዕገቶሙኒ ለእስራኤል ተበ እሱ በመካኖሙ እምዐረቢሃ ለገባእን ።

የእስራኤል ወንዶች ሁሉ ከቦታቸው ተነሥተው በበ ዓልታምር ተዋጉ ፡ የእስራኤልም ከባቢዎች በገባእን ግራ በቦታቸው ተዋጉ ።

፴፬ ወገብኡ እንተ ቅድሜሃ ለገባእን እልፍ ብእሲ ኅሩያን እምእስራኤል ወጸንዐ ቀትል ፡ ወእሙንቱሰ ኢያአመሩ ከመ በጽሐቶሙ እከዮሙ ።

ከእስራኤል የተመረጡ እልፍ ሰዎች በገባእን አፍዛ ገር ተመለሱ ፡ ሰልፉም (ውጊያው) ጸና ፡ እነሳቸው ግን የክ ፉታቸው ፍዳ እንደደረሰችባቸው አላወቁም ።

፴፭ ወአውደቆሙ እግዚአብሔር ለብንያሚ ቅድመ እስራ ኤል ወቀተልዎሙ ደቂቀ እስራኤል ለብንያሚ ክልኤቱ እልፍ ወሐምስ ምእት ወአሐዱ ምእት ፡ ወኵሎሙ እለ ይፀውሩ ኲናተ ።

እግዚአብሔርም የብንያሚን ልጆች በእስራኤል ፊት ጣላቸው ፡ የእስራኤል ልጆች ሁለት እልፍ ከአምስት ሺሕ ከንድ መቶ የብንያሚን ልጆች ገደሉዋቸው ሁሉም ለጦር የደረሱ ናቸው ።

፴፮ ወርእየ ብንያሚ ከመ ተቀትለ ወወሀብዎሙ እስራኤል መካነ እስመ ተአመኑ በማዕገቶሙ ዘሜሙ ላዕለ ገባእን ።

የብንያም ልጆች ድል እንደተነሡ አዩ ፡ እስራኤልም በገባእን በኖሩዋቸው ከባቢዎች (ድብቅ ጦር) ታምነዋልና ቦታን ለቀቁላቸው (ሰጧቸው) ።

፴፯ ወሖሩ እልክቱ እለ ዐገቱ ወቀተልዋ ለሀገር በአፈ ሐፂን ።

እነዚያም ከባቢ ጦሮች ሂደው አገሪቱን በጦር አጠ ፉት ። ዘፀ፡ ፲፱ ፲፫ ። ኢያ፡ ፰ ፲፱ ።

፴፰ ወአዘዝዎሙ እስራኤል ለእለ የዐግቱ ከመ በሐፂን ይቅትልዎሙ ወያዕርግዎ ለጢሰ ሀገር ከመ ማኅፈድ ።

እስራኤልም በጦር ያጠፉዋቸው ዘንድ የአገሪቱንም ጢስ እንደ ግንብ ያወጡት ዘንድ እነዚያን የከበቡ ሰዎች አዘዙቸው ።

፴፱ ወተመይጡ ሰብአ እስራኤል በውስተ ቀትል ወለብን ያምሰ አኀዝዎ ይቅትልዎ ሰብአ እስራኤል ወየአክሉ ስድ ስተ ምእተ ብእሴ እስመ ይቤ እንበለ ይቀትሉኒ ቀተልክ ዎሙ በቅድሜየ ከመ ቀትል ዘቀዲሙ ።

የእስራኤል አርበኞች ወደ ሰልፉ ተመለሱ በፊቴ እንደ ቀድሞው ሰልፍ ሳይጠፉኝ አጠፋቸዋለሁ ብሏልና ፡ የእስ ራኤል አርበኞች ብንያሚን ያጠፉ ዘንድ ጀመሩ ፡ እነዚህም ስድስት መቶ ሰዎች ያህሉ ነበሩ ። መሳ፡ ፳ ፴፩ ።

፵ ወዝክቱ ጢሰ ማኅፈድ የዐርግ እምሀገር ከመ ዐምድ ወነጸረ ብንያሚ ድኅሬሁ ወናሁ ዐርገ ጥፍአተ ሀገር ው ስተ ሰማይ ።

ያም የግንቡ ጢስ እንደ ምሰሶ ከከተማው ቀጥ ብሎ ወጣ ፡ የብንያምም ወገን ወደኋላው በየ ጊዜ እነሆ የአገሩ ጥፋት በዝቶ እንደተደረገ ዐወቀ ። መሳ፡ ፳ ፴፰ ።

፵፩ ወተመይጡ ሰብአ እስራኤል ወተወላወሉ ሰብአ ብን ያሚ ወርእዩ ከመ በጽሐቶሙ እከዮሙ ።

የእስራኤል ወገኖች በተመለሱ ጊዜ የብንያም ልጆች ተሸበሩ ፡ የክፋታቸውም ፍዳ እንደረሰችባቸው ዐወቁ ።

፵፪ ወነትዑ ቅድሜሆሙ ለእስራኤል ውስተ ፍኖተ ገዳ ም ፡ ወበጽሐሙ ቀትል ወእለሂ እምሀገር ቀተልዎሙ በማ እከሎሙ ።

ከእስራኤል ፊት ወደ ምድረ በዳ ሸሹ ፡ ሰልፍም ደረ ሰባቸው በሀገርም ያሉ ሰዎች በመከከላቸው አጠፉዋቸው ። መሳ፡ ፩ ፵፭ ፡ ኢያ፡ ፰ ፲፭ - ፳፬ ።

፵፫ ወቀተልዎሙ ለብንያሚ ወአጥፍእዎሙ ወደምሰስ ደምሰስዎሙ በቅድመ ገባእን መንገለ ጽባሒሃ ።

የብንያሚንም ልጆች ወግተው አጠፉዋቸው ፡ በገ ባእንም አንጻር በምሥራቋ ፈጽመው አጠፉዋቸው ። ዘኍ፡ ፲ ፴፫ ።

፵፬ ወወድቁ እምብንያሚ እልፍ ወሰማንያ ምእት ብእሲ ወኵሎሙ እሉ ጽኑዓን ሰብእ ።

ከብንያሚ ልጆች ወገን እልፍ ከስምንት ሺሕ ሰዎች ወደቁ (ሞቱ) ፡ እነዚህም ሁሉ አርበኞች ነበሩ ።

፵፭ ወጐዩ ኀበ ኰኵሐ ሬሞን ወአርአይዎሙ በፍኖት ኀ ምሳ ምእተ ብእሲ ወዴገንዎሙ ወቀተልዎሙ እስከ ጌዴ ኦም ወቀተሉ እምኔሆሙ ዕሥራ ምእተ ብእሲ ።

ወደ ሬሞን ዋሻም ሸሹ ፡ በጐዳናም አምስቱን ሺሕ ሰዎች ለቀሟቸው ተከትለውም እስከ ጌዴኦም ድረስ አጠ ፏቸው ፡ ከነሳቸውም ሁለት ሺሕ ገደሉ ።

፵፮ ወኮኑ ኵሎሙ እለ ወድቁ እምብንያሚ ክልኤቱ እልፍ ወሐምሳ ምእት ወእሐዱ ምእት ብእሲ እለ ይፀውሩ ኲና ተ በይእቲ ዕለት ወኵሎሙ እሉ ሰብእ ጽኑዓን ።

በዚያችም ቀን ከብንያም ወገን የሞቱ ለጦር የደረሱ ሰዎች ሁለት እልፍ አምስት ሺሕ ከአንድ መቶ ሆኑ ፡ እነዚህም ሰዎች ሁሉ አርበኞች ነበሩ ። መሳ፡ ፳ ፵፭ - ፵፬ ።

፵፯ ወነትዑ ወጐዩ ውስተ ኰኵሐ ሬሞን ስድስቱ ምእት ብእሲ ወነበሩ ውስተ ኰኵሐ ሬሞን አርባዕተ አውራኀ ።

ስድስት መቶም ሰዎች ወደ ሬሞን ዋሻ ፈጽመው ሸሹ ፡ በዚያ በሬሞንም ዋሻ አራት ወር ተቀመጡ ።

፵፰ ወዐጸውዎሙ ሰብአ እስራኤል ለደቂቀ ብንያሚ ወቀ ተልዎሙ በአፈ ሐፂን ወሀገሮሙኒ እውዐዩ ወእንስሳሆ ሙኒ ወኵሎ ዘተረክበ ውስተ ሀገር አህጉሪሆሙኒ እለ ረከቡ አውዐዩ በእሳት ።

የእስራኤል ሰዎች የብንያሚን ልጆች ዘጉባቸው ፡ በጦርም አጠፉዋቸው ሀገራቸውንም ከብቶቻቸውንም በሀ ገር የተገኘውንም ሁሉ አጠፉ ፡ ያገኙዋቸው አምበዎቻ ቸውን በእሳት አቃጠሉዋቸው ። ዘፍ፡ ፲፱ ፲፭ ።

## ምዕራፍ ፳፩ ።

፩ ወተማሐሉ ሰብአ እስራኤል በመሴፋ እንዘ ይብሉ ከመ ኢየሀብ ብእሲ እምኔነ ወለቶ ለብንያሚ ያስተዋስብ ።
፪ ወሖሩ ኵሉ ሕዝብ ውስተ ቤቴል ወነበሩ እስከ ሠርክ ቅድመ እግዚአብሔር ወፀርሑ ወበከዩ ዐቢየ ብካየ ።
፫ ወይቤሉ ለምንት እግዚኦ ከነት ዛቲ እኪት በውስተ እስራኤል ከመ ትፃእ ዮም አሐቲ ሕዝብ እምእስራኤል ።
፬ ወእምዝ በሳኒታ ጌሡ ሕዝብ ወነደቁ በህየ ምሥዋዐ ወአዕረጉ መሥዋዕተ መድኀኒት ።
፭ ወይቤሉ ደቂቀ እስራኤል መኑ ዘኢዐርገ እማኅበር እምኵሉ ሕዝበ እስራኤል ኀበ እግዚአብሔር እስመ ዐቢይ መሐላሆሙ ከመ ዘኢዐርገ ኀበ እግዚአብሔር ውስተ መሴፋ ሞተ ለይሙት ይቤሉ ።
፮ ወተኣረቅዎ ደቂቀ እስራኤል ለብንያሚ እኁሆሙ ወይቤሉ ትወፅእ ዮም አሐቲ ሕዝብ እምእስራኤል ።
፯ ምንተ እንከ ንሬስዮሙ ለእለ ተርፉ በእንተ አንስት ናሁ መሐልነ ንሕነ በእግዚአብሔር ከመ ኢንሁቦሙ እም አዋልዲነ ያውስቡ ።
፰ ወይቤሉ መኑ እምአኃዊነ ሕዝበ እስራኤል ዘኢዐርገ ኀበ እግዚአብሔር ውስተ መሴፋ ወናሁ አሐዱ ብእሲ ኢመጽአ እምኔ ኢያቢስ ዘገለአድ ውስተ ማኅበሮሙ ።
፱ ወተፈቀዱ ሕዝብ ወናሁ አሐዱ ብእሲ ዘእምኢያቢስ ዘገለአድ ኢሀለወ ።
፲ ወለአኩ ህየ ማኅበሮሙ እልፈ ወዕሥራ ምእተ ብእሴ እምደቂቀ ኀይል ወአዘዝዎሙ እንዘ ይብሉ ሑሩ ወቅትሉ ኵሎ እለ ይነብሩ ውስተ ኢያቢስ ዘገለአድ በአፈ ሐፂን አንስተኒ ወሕዝበኒ ።
፲፩ ወከመዝ ገበሩ ኵሎ ተባዕተ ወኵሎ አንስተ እለ የአምራ ብእሴ ቀተሉ ።
፲፪ ወረከቡ እምእለ ይነብሩ ውስተ ገለአድ አርባዕተ ምእተ አዋልደ ደናግለ እለ ኢያእመራ ብእሴ ወአምጽእዎን ውስተ ትዕይንት ውስተ ሴሎ ውስተ ምድረ ከነአን ።
፲፫ ወለአኩ ኵሉ ማኅበሮሙ ኀበ ብንያሚ እለ ውስተ ኰኵሐ ሬሞን ወጸውዕዎሙ በሰላም ።
፲፬ ወገብኡ ብንያሚ ኀበ ደቂቀ እስራኤል በእማንቱ መዋዕል ወወሀብዎሙ አንስተ ዘአሕየዉ እምአንስተ ኢያቢስ ዘገለአድ ወሠምሩ በዝንቱ ።
፲፭ ወሕዝብኒ ተኳነንዎሙ ለብንያሚ እስመ ገብረ እግዚአብሔር ቀትለ በውስተ ሕዝበ እስራኤል ።
፲፮ ወይቤሉ ሊቃናተ ማኅበር ምንተ ንግበር በእንተ እለ ተርፉ ሕዝብ በበይነ አንስት እስመ ጠፍአ አንስት እምብንያሚ ።
፲፯ ወይቤሉ ርስት ተርፈ ለብንያሚ ወኢትደምስስ ሕዝብ እምእስራኤል ።
፲፰ ወንሕነሰ ኢንክል ውሂቦቶሙ አንስተ እምአዋልዲነ እስመ መሐሉ ደቂቀ እስራኤል እንዘ ይብሉ ርጉም ውእቱ ዘይሁብ ብእሲተ ለብንያሚ ።

## ምዕራፍ ፳፩ ።

፩ የእስራኤል ሰዎች ከኛ አንድ ሰው ሴት ልጁን ያጋባ ዘንድ ለብንያም ልጆች እንዳይሰጥ ብለው ተማማሉ ።
፪ ሕዝቡም ሁሉ ወደ ቤቴል ሄደው እስከ ሠርክ ድረስ በእግዚአብሔር ፊት ጮኹ፤ ፈጽመውም አለቀሱ ።
፫ አቤቱ፤ ከእስራኤል አንዲቱ ወገን አሁን ተለይታ ትወጣ ዘንድ በእስራኤል ዘንድ ይህች ክፉ ለምን ሆነች አሉ።
፬ ከዚህ በኋላ ሕዝቡ በማግሥቱ ገሥግሠው ሄደው በዚያ መሠውያን ሠሩ፤ በዚያም የድኅነት መሥዋዕትን ሠዉ።
፭ የእስራኤልም ልጆች ከእስራኤል ዘንድ ወደ መሴፋ ያልወጣ ሰው ይሞት ዘንድ ይሙት ብለው የተማማሉት መሐላቸው ጽኑ ነውና፤ ከእስራኤል ወገኖች ሁሉ ወደ እግዚአብሔር ያልወጣ ሰው ማነው፤ አሉ ።
፮ የእስራኤል ልጆች አሁን ከእስራኤል አንዲቱ ወገን ተለይታ ትወጣለችን ብለው የብንያምን ልጆች ታረቁዋቸው ።
፯ ከልጆቻችን ያገቡ ዘንድ እንዳንሰጣቸው እነሆ እኛ በእግዚአብሔር ምለናልና ከሞት ለቀሩ ሰዎች ሴት ስለሌላቸው እንግዲህ ምን እናደርጋቸዋለን፤ አሉ ።
፰ ከወንድሞቻችን ከእስራኤል ወገኖች ወደ እግዚአብሔር ወደ መሴፋ ያልወጣ ማነው፤ አሉ፤ እነሆ ከገለዓድ ዕጣ ከኢያቢስ የሚሆን አንድ ሰው ወደ እስራኤል ወገኖች አልመጣም ነበር ። ፩ ሳሙ፣ ፲፩ ፩ ።
፱ ሕዝቡም ተቈጣጠሩ እነሆ ከገለዓድ ዕጣ ከኢያቢስ ወገን የሚሆን አንድ ሰው አልነበረም ።
፲ ከአርበኞች ልጆች ወገን እልፍ ከሁለት ሺሕ ሰዎች የሚሆኑ ወገኖችም ሂዱና የገለዓድ ዕጣ በምትሆን በኢያቢስ የሚኖሩ ሰዎችን ሁሉ በጦር ግደሉ ብለው ወደዚያ ላኩ፤ ሴቶቹንም ሕዝቡንም አጥፉ ብለው አዘዙዋቸው ።
፲፩ እነሳቸውም እንዲህ አደረጉ ባል ያገቡ ሴቶችን ሁሉና ወንዶቹንም ሁሉ ገደሉ ። ዘኍ፣ ፴፩ ፲፯ ዘዳ፣ ፯ ፪ ።
፲፪ በገለዓድ የሚኖሩ ባል ያላገቡ አራት መቶ ደናግሎችን አገኙ፣ በከነዓን ምድር ወዳለችው ወደ ሴሎ ወደ ሰፈሩ አመጧቸው ። ኢያ፣ ፲፰ ፩፣ ፳፩ ፪ ።
፲፫ ወገኖቻቸው ሁሉ በሬሞን ዋሻ ወዳሉ ወደ ብንያም ልጆች ልከው በፍቅር ጠሩዋቸው ። ዘዳ፣ ፳ ፲ ።
፲፬ የብንያምም ልጆች በዚያ ወራት ወደ እስራኤል ልጆች ተመለሱ፣ የገለዓድ ዕጣ በምትሆን ከኢያቢስ ያዳኗቸው ሴቶችንም ሰጡዋቸው፤ በዚህም ተስማሙ ።
፲፭ እግዚአብሔር ከእስራኤል ወገኖች መከከል ሰልፍን አድርጎ ነበርና ሕዝቡ የብንያሚን ልጆች ተወቃቀሷቸው።
፲፮ የማኅበሩም ሽማግሌዎች ከብንያም ነገድ ሴቶች ጠፍተዋልና ከሞት ስለ ቀሩ ሰዎች የሴቶችን ነገር ምን እናድርግ፤ አሉ ።
፲፯ ለብንያም ልጆች ርስት ቀረባቸው አንዲቱ ወገን ከእስራኤል ተለይታ አትጥፋ ።
፲፰ ለብንያም ልጆች ሚስት የሚሰጥ ሰው ርጉም ይሁን ብለው የእስራኤል ልጆች ምለዋልና፤ እኛም ከልጆቻችን ሚስት መስጠት አንችልም አሉ ። መሳ፣ ፳፩ ፩፣ ፲፩ ፴፭።

| | | |
|---|---|---|
| ወይቤሉ በዓለ እግዚአብሔር በሴሎ እመዋዕል በበመዋዕሊሁ ውእቱ እመንገለ መስዕ ለቤቴል ወበጽባሒሃ ለፍኖት እንተ ታዐርግ እምቤቴል ለሰቂማ ወእመንገለ አዜብ ለሌብና ። | ፲፱ | ከአንዱ ዘመን በየወራቱ የሚደረግ የእግዚአብሔር በዓል ከቤቴል ወደ ሰቂማ በምታወጣ ጐዳና ምሥራቅና በቤቴል ግራ አንጻር በሌብናም ግራ ባለች በሴሎ ይደረጋል አሉ ፤ መሳ፡ ፲፩ ፹፡ ፩ ሳሙ፡ ፩ ፫ ። |
| ወአዘዝዎሙ ለደቂቀ ብንያሚ ወይቤልዎሙ ሑሩ ወተኀብኡ ውስተ ዐፀደ ወይን፤ ወተዐቀቡ አዋልዲሆሙ ለእለ ይነብሩ ውስተ ሴሎም እንዘ ይትዋነያ በመሰንቆ ። | ፳ | የብንያምንም ልጆች ሂዳችሁ በወይን ቦታ ተሠወሩ በሴሎም የሚኖሩ ሰዎች ልጆቻቸውን መሰንቆ እየመቱ ሲጫወቱ ተጠባበቁ ። |
| ወትወፅኡ እምዓፀደ ወይን ወምስጡ ለክሙ አንስተ እምአዋልደ ሴሎም ወእትዉ ውስተ ብንያሚ ። | ፳፩ | ከወይን ቦታ ወጥታችሁም ከሴሎም ልጆች ለናንተ ሚስት ነጥቃችሁ ወደ ብንያም ዕጣ ተመለሱ ብለው አዘዙዋቸው ። ዘፀ፡ ፲፭ ፳ ። ፩ ሳሙ፡ ፲፰ ፯፡ ፳፩ ፲፩ ። |
| ወለእመ መጽኡ አበዊሆን ወአኀዊሆን ይሰነኑክሙ ንብሎሙ መሐርዎሙ እስመ ኢያውዕኡ አንስቲያሆሙ እምቀትል እስመ አከ አንትሙ ዘወሀብክምዎሙ በእማንቱ መዋዕል ኢትነስሑ ። | ፳፪ | ወንድሞቻቸውና አባቶቻቸውም ሊጣሉዋችሁ ቢመጡ ሚስቶቻቸውን ወደ ሰልፍ አላወጡምና ማሩዋቸው በዚያ ወራት እናንተ የሰጣችኋቸው አይደለምና አትጸጸቱ እንላቸዋለን አሉዋቸው ። |
| ወገብሩ ከማሁ ደቂቀ ብንያሚ ወነሥኡ አንስተ በኍላቄሆሙ እምእለ ይትዋነያ ወተማሰጥዎን ወአተዉ ወገብኡ ውስተ ርስቶሙ፤ ወነደቁሎሙ አህጉረ ወነበሩ ውስቴቶን። | ፳፫ | የብንያምም ልጆች እንዳሏቸው አደረጉ፤ ከሚጫወቱት ልጆች በቍጥራቸው መጠን ሴቶችን ተጣቅሰው ይዘው ወደ ርስታቸው ተመለሱ ፤ ለነሳቸውም ከተሞችን ሠርተው በውስጣቸው ተቀመጡ ። |
| ወአተዉ እምህየ ደቂቀ እስራኤል ብእሲ ብእሲ ውስተ ሕዝቡ ወውስተ ነገዱ ወአተዉ እምህየ ብእሲ ብእሲ ውስተ ርስቱ ። | ፳፬ | የእስራኤልም ልጆች ከዚያ አንዱም አንዱም ሰው ወደ ወገኑ ወደ ነገዱ ተመለሰ፤ ከዚያም አንዱም አንዱም ሰው ወደ ርስቱ ገቡ ። |
| ወበእማንቱ መዋዕል አልቦሙ ንጉሥ ለእስራኤል ብእሲ ብእሲ ዘአደሞ ቅድመ አዕይንቲሁ ይገብር ። | ፳፭ | በዚያም ወራት ለእስራኤል ንጉሥ አልነበራቸውምና አንዱም አንዱም ሰው በፊቱ የወደደውን ያደርግ ነበር ። |

ተፈጸመ አሪት ዘመሳፍንት፣
ወስብሐት ለእግዚአብሔር ዘአልበቱ ጥንት ወተፍጻሜት፣
አሜን።

የመሳፍንትን ነገር የሚናገር መጽሐፍ ደረሰ ተፈጸመ፣
ጥንትና ፍጻሜ ለሌለው ለእግዚአብሔር ለዘለዓለሙ ክብር ምስጋና ይግባው።
አሜን።

# ኦሪት ዘሩት

## ምዕራፍ ፩ ።

፩ ወኮነ በመዋዕለ ይኴንኑ መሳፍንት መጽአ ረኃብ ውስ
ተ ብሔር ወሖረ አሐዱ ብእሲ እምቤተ ልሔም ዘይሁዳ
ከመ ይንበር ውስተ ሐቅለ ሞአብ ውእቱ ወብእሲቱ ወክ
ልኤቱ ደቂቁ ።
፪ ወስሙ ለውእቱ ብእሲ አቤሜሌክ ወስመ ብእሲቱ ኖኃ
ሚን ወአስማቲ ደቂቁ ክልኤቱ መሐሎን ወኬሌዎን ኤፍ
ራታውያን እምቤተ ልሔም ዘይሁዳ ወሖሩ ውስተ ሐቅለ
ሞአብ ወነበሩ ህየ ።

፫ ወሞተ አቤሜሌክ ምታ ለኖኃሚን ወተርፈት ባሕቲታ
ወደቂቃ ክልኤሆሙ ።
፬ ወነሥኡ ሎሙ አንስተ ሞአባውያተ ፥ ስማ ለአሐቲ
ዑርፋ ፥ ወስማ ለካልእታ ሩት ፥ ወነበሩ ህየ ወአከለ ዐሠ
ርተ ዓመተ ።
፭ ወሞቱ ክልኤሆሙ ውሉዳ ለኑኃሚን መሐሎን ወኬ
ሌዎን ወተርፈት ይእቲ ብእሲት እምታ ወእምክልኤሆሙ
ደቂቃ ።
፮ ወተንሥአት ይእቲ ወክልኤሆን መራዕዊሃ ወተመይ
ጠት እምሐቅለ ሞአብ እስመ ሰምዐት ከመ ተሣሀሎሙ
እግዚአብሔር ለሕዝቡ ከመ የሀበሙ እክለ ።
፯ ወወፅአት እምውእቱ መካን ኀበ ይነብራ ክልኤሆን
መራዕዊሃ ምስሌሃ ወሖራ ውስተ ፍኖት ከመ ይእትዋ ው
ስተ ምድረ ይሁዳ ።
፰ ወትቤሎን ኑኃሚን ለመራዕዊሃ ሑራ እትዋ አብያተ
አበዊክን ወእማቲክን ፥ ወይግበር እግዚአብሔር ምሕረቶ
ምስሌክን ከመ ገበርክን ምሕረተ ምስለ እለ ሞቱ ወም
ስሌየ ።
፱ ወየሀብክን እግዚአብሔር ትርከባ ምሕረተ ወዕረፍተ
ውስተ አብያተ አምታቲክን ወሰዐመቶን ።
፲ ወጸርሓ ወበክያ ወይቤላሃ ምስሌኪ ንገብእ ውስተ
ሕዝብኪ ።
፲፩ ወትቤሎን ኑኃሚን እትዋ አዋልድየ ለምንት ትመጽአ
ምስሌየ ቦኑ ዘብየ ዓዲ ውሉድ ውስተ ከርሥየ እለ ያወስ
ቡክን ።
፲፪ እትዋ እንከሰ አዋልድየ እስመ ረሣዕኩ እምአው
ስቦ ዘእምወለድኩ ወሉደ ወትጸንሓሆሙኑ እስከ አመ
ይልህቁ ።

## ምዕራፍ ፩ ።

፩ መሳፍንት በሚገዙበት ወራት እንዲህ ሆነ ፥ ረኃብ በአ
ገር መጣ ፥ የይሁዳ ክፍል ከምትሆን ከቤተ ልሔም አንድ
ከሚስቱና ከሁለት ልጆቹ ጋራ በሞዓብ አውራጃ ይኖር
ዘንድ አንድ ሰው ሄደ ። መሳ፥ ፪ ፲፯፥ ፲፯ ፳ ።
፪ የዚያም ሰው ስሙ አቤሜሌክ ይባላል ፥ የሚስቱም
ስም ኑኃሚን ይባላል ፥ የሁለቱም ልጆቹ በማቸው መሐሎን
ኬሌዎን ይባላል ፥ እነዚህም የይሁዳ ዕጣ ከምትሆን ከቤ
ተ ልሔም ወገን የሚሆኑ ኤፍራታውያን ናቸው ወደ ሞዓ
ብ አውራጃ ሄደው በዚያ ተቀመጡ ። ዘፍ፥ ፴፭ ፲፱ ።
፫ የኖኃሚን ባልዋ አቤሜሌክ ሞተ ፥ ያችም ሴት ከሁለቱ
ልጆቿ ጋራ ቀረች ።
፬ እነርሱም ከሞዓባውያን ሴቶች ሚስት አገቡ ፥ የአን
ዲቱ ስሟ ዑርፋ የሁለተኛይቱ ስም ሩት ይባላል ፥ በዚያም
ኖሩ ፥ ዓሥር ዓመት ያህል ሆነ ።
፭ ሁለቱ የኑኃሚን ልጆች ኬሌዎንና መሐሎን ሞቱ ፥
ያች ሴት ከባሏና ከሁለቱ ልጆቿ ተለይታ ቀረች ።

፮ እሷ ከሁለቱ ምራቶቿ ጋራ ተነሣች ፥ እኽል ይሰጣ
ቸው ዘንድ እግዚአብሔር ወገኖቹን ይቅር እንዳላቸው
ሰምታለችና ከሞዓብ አውራጃ ተመለሰች ።
፯ ከእሷ ጋራ ሁለቱ ምራቶቿ ከሚኖሩበት ቦታ ወጥታ
ወደ ይሁዳ ዕጣ ይሄዱ ዘንድ መንገዳቸውን ሄዱ ።

፰ ኑኃሚንም ምራቶቿን ሂዱና ወደ እናቶቻችሁና ወደ
አባቶቻችሁ ቤት ግቡ ፥ ለኔና ለሞቱትም ባሎቻችሁ በጎ
ነትን እንዳደረጋችሁ እግዚአብሔር ቸርነቱን ያድር
ግላችሁ ። ኢያ፥ ፪ ፲፪ ፥ መሳ፥ ፩ ፳፬ ።
፱ በባሎቻችሁ ቤት ዕረፍትን ታገኙ ዘንድ እግዚአብ
ሔር ቸርነቱን ይስጣችሁ ብላ ሳመቻቸው ።
፲ እነሱም ድምጻቸውን ከፍ አድርገው አለቀሱ ፥ ከን
ቺም ጋራ ወደ ወገኖችሽ እንመለሳለን (እንሄዳለን) አሏት ።
፲፩ ኑኃሚንም ልጆቼ ! ከኔ ጋራ ለምን ትመጣላችሁ ፤
ተመለሱ በውኑ አሁን በሆዴ የሚያገቡዋችሁ ልጆች
አሉኝን ፤ ። ዘፍ፥ ፴፰ ፲፩ ፥ ዘዳ፥ ፳፭ ፭ ።
፲፪ ከማግባት አርጅቻለሁና እንግዲህ ወዲህስ ልጆቼ !
ተመለሱ ተስፋ አለኝ ብዬ ባል በገባ እስኪያድጉ ድረስ
ተጠብቁዋቸዋላችሁን ! ።

| | | |
|---|---|---|
| ፲፫ | ወታጸንዓ ርእሰክን ወኢትትዋሰባ አልቦ አዋልድየ፣ እስመ መረረተኒ ነፍስየ ጥቀ ፈድፋደ እምኔክን እስመ ወፅአት እምኔየ እደ እግዚአብሔር ። | ስለ እነርሱስ ባል ማግባት ትተዋላችሁን፤ ከናንተ የተነሣ ልቡናዬ ፈጽማ አዝናብኛለችና የእግዚአብሔርም ረድኤት ከኔ ተለይታለችና ልጆቼ! እንዲህ አይደለም ተመለሱልኝ አለቻቸው ። መሳ፥ ፪ ፲፭ ። ኢዮብ ፲፱ ፳፩ ። |
| ፲፬ | ወጸርሐ ከዐበ ወበከያ ወሰዐመታ ለዑርፍ ሐማታ ወተ መይጠት ኀበ ሕዝባ ወሩትሰ ተለወታ ። | ዳግመኛም ድምፃቸውን ከፍ አድርገው አለቀሱ፣ አማቷም ዑርፋን ሳመቻት ወደ ዘመዶቿም ተመለሰች፥ ሩት ግን ተከተለቻት ። |
| ፲፭ | ወትቤላ ኑኃሚን ለሩት ናሁ አተወት ካልእትኪ ኀበ ሕዝባ ወኀበ አማልክቲሃ እትዊ አንቲኒ ምስለ ካልእትኪ ። | ኑኃሚንም ሩትን እነሆ በልንጀራሽ ወደ ወገኖቿና ወደ ጣኦቶቿ ተመለሰች፣ አንቺም ከባልንጀራሽ ጋራ ተመለሺ አለቻት ። ዘፍ፥ ፴፪ ፳፯ ። ኢያ፥ ፳፬ ፭ ። |
| ፲፮ | ወትቤላ ሩት ኢይትከሃለኒ ከመ እኅድጊ ወከመ እት መየጥ እምድኅሬኪ ኀበ ሖርኪ አንቲ አሐውር ወኀበ ኀደ ርኪ አኀድር፣ ሕዝብኪ ሕዝብየ ወአምላክኪ አምላክየ ወበ ኀበ ሞትኪ እመውት ወህየ እትቀበር ። | ሩትም አለይሽና እንችንም ትቼ እመለስ ዘንድ አይ ቻለኝም አንቺ ከሄድሽበት እሄዳለሁ፣ ካደርሽበትም አድራለሁ ወገኖችሽም ወገኖቼ ፈጣሪሽም ፈጣሪዬ ነው ከምትሸበት እሞታለሁ፣ በዚያም እቀበራለሁ አለቻት ። |
| ፲፯ | ከመዝ ለይረስየኒ እግዚአብሔር ወከመዝ ለእኩን ከመ አልቦ ዘይፈልጠኒ እምኔኪ ዘእንበለ ሞት ። | ከሞት በቀር ካንቺ የሚለየኝ እንደሌለ ብላ የያዘች ውን ጥላ እንዲህ ይጣለኝ፣ እግዚአብሔር ያንቺ ሞት ለኔ ያድርገው አለቻት ። ፩ ሳሙ፥ ፫ ፲፯፣ ፲፬ ፵፬ ። |
| ፲፰ | ወሰበ ርእየት ኑኃሚን ከመ አጽንዐት ልባ ለሐዊር ምስሌሃ ኀደገት እንከ ብሂሎታ ። | ኑኃሚንም ከርሷ ጋራ ለመሄድ ልቡናዋን እንዳጸናች በየች ጊዜ ከዚያ በኋላ ተመለሺ ማለትን ተወች ። |
| ፲፱ | ወሖራ ክልኤሆን እስከ በጽሓ ቤተ ልሔም ወደምፀት ኵላ ሀገር በእንቲአሃ ወይቤልዋ ሕያውትኑ አንቲ ኑኃሚን | ሁለቱም ቤተ ልሔም እስኪደርሱ ድረስ ሄዱ፣ መም ጣቷም በሀገሩ ሁሉ ተሰማ ኑኃሚን ደኅና ነሺ፤ አሉዋት። |
| ፳ | ወትቤሎን ኢትሰምያኒ ኑኃሚን አላ ስምያኒ መራረ እስመ መረረኒ ፈድፋደ ወብዙኀ ። | እጅግ ፈጽሜ አዝኛለሁና ኑኃሚን ያዘነች በሉኝ እንጂ ደስ ያላት አትበሉኝ ። ዘፀ፥ ፲፭ ፳፫ ። |
| ፳፩ | ወአንሰ ምልእትየ ሖርኩ ወዕራቅየ አግብአኒ እግዚአ ብሔር ለምንት ትብላኒ ኑኃሚን እንዘ እግዚአብሔር አኅ ሠረኒ ወፈድፋደ አሕመመኒ ። | እኔ ብዙ ሁኜ ሄድኩ እግዚአብሔር በዶዬን መለሰኝ እግዚአብሔር አዋርዶኝ ሳለ ፈጽሞም አሳዝኖኝ ሳለ ለምን ደስ ያላት ትሉኛላችሁ፤ አለቻቸው ። ኢዮብ ፩ ፳፩ ። |
| ፳፪ | ወገብአት ኑኃሚን ወሩት መርዓታ ሞአባዊት ወአተዋ እምሐቅለ ሞአብ ወበጽሓ ውስተ ቤተ ልሔም አመ ቀዳሚ ማእረረ ሰገም ። | ኑኃሚንም ከሞዓባዊት ሴት ከምራቷ ከሩት ጋራ ከሞ ዓብ አውራጃ ተመልሳ ገባች፣ መጀመሪያ ገብስ በሚለቀ ምበት ወራት ወደ ቤተ ልሔም ደረሱ ። ሩት ፫ ፳፫ ። |
| | ምዕራፍ ፪ ። | ምዕራፍ ፪ ። |
| ፩ | ወቦቱ ለኑኃሚን ብእሲ ዘየአምሮ ለምታ ወውእቱሰ ብእሲ ጽኑዕ ወከሀሊ እምአዝማዲሁ ውእቱ ለአቤሜሌክ ወስሙ ቦአስ ። | ኑኃሚን ባሏን (በመውረስ) የሚያውቀው የሚዘመ ደው ሰው ነበራት፣ ያ ሰው ግን የጸና ከአቤሜሌክ ወገን የሆነ ኃያል ሰው ነበር፣ ስሙም ቦአስ ይባላል ። |
| ፪ | ወትቤላ ሩት ሞአባዊት ለኑኃሚን እሑርኑ ው ስተ ገራህት እእሪ እክለ ኀበ እለ ረከብኩ ሞገሰ ወት ቤላ ሑሪ ወለትየ ። | የሞዓብ ወገን ሴት የምትሆን ሩት ኑኃሚንን ባለሟል ነትን ከገኘሁበት ዘንድ እኽልን ለመልቀም ልሂድን፤ አለ ቻት፣ ይሁን ልጂ ሂጂ አለቻት ። ዘዳ፥ ፳፬ ፲፱ ። |
| ፫ | ወሖረት ወአረየት እምውስተ ገራህት እንዘ ትተል ዎሙ ለእለ የዓፅዱ ወበጽሐት ውስተ አሐዱ ኀብር እምገ ራህቱ ለቦአስ ዘእምዘመዱ ለአቤሜሌክ ። | ሂዳም የሚያጭዱትን ሰዎች እየተከተለች ከእርሻው ለቀመች ከአቤሜሌክ ዘመድ ከቦአስ እርሻ ወዳንዱ ወገን ደረሰች ። |
| ፬ | ወመጽአ ቦአስ እምነ ቤተ ልሔም ወይቤሎሙ ለእለ የዐፅዱ እግዚአብሔር ምስሌክሙ ወይቤልዎ ይባ ርከ እግዚአብሔር ። | ቦአስም ከቤተ ልሔም መጥቶ እኽል የሚያጭዱትን ሰዎች እግዚአብሔር ከናንተ ጋር ይሁን አላቸው፣ እነሱም እግዚአብሔር ያክብርህ (ይባርክህ) አሉት ። |
| ፭ | ወይቤሎ ቦአስ ለወልዱ ዘይቀውም ላዕለ እለ የዐፅዱ እንተ መኑ ዛቲ ወለት ። | ቦአስ በሚያጭዱት ሰዎች ላይ የተሾመው ብላቴናውን ይህች የማን ልጅ ናት፤ አለው ። |
| ፮ | ወአውሥአ ውእቱ ወልድ ዘይቀውም ላዕለ እለ የዐ ፅዱ ወይቤሎ እንታክቲ ወለት ሞአባዊት እንተ ገብአት ምስለ ኑኃሚን እምሐቅለ ሞአብ ። | ያም በአጫጆዎች ላይ የተሾመው ብላቴና ከሞዓብ አገር ከኑኃሚን ጋራ የመጣች ያች የሞዓብ ሴት የምት ሆን ልጅ ናት አለው ። ሩት ፩ ፲-፳፪ ። |

፯ ወትቤ እእሬ ወአስተጋብእ እምዘወድቀ እምከላስስት እምድኅሬሆሙ ለእለ የዐፅዱ ወመጽአት ወቆመት እምንግህ እስከ ይእዜ ወኢኀደገት ንስቲተኒ እምውስተ ገራህት ።

፰ ወይቤላ ብኤዝ ለሩት ኢሰማዕኪኑ ወለትየ ኢትበኢ ውስተ ገራህት ባዕድ ለአስተጋብኦ ወኢትሑሪ እምዝየ ትልዊዮን ለአዋልድየ ።

፱ ወነጽሪ ውስተ ገራህት ኀበ የዐፅዱ ወትልውዮሙ ናሁ አዘዝኩ ደቀ ከመ አልቦ ዘይለክፈኪ ወእመኒ ጸማእኪ ሑሪ ኀበ ንዋይ ወስተዪ እምዘአምጽኡ ደቅ ።

፲ ወወድቀት በገጻ ወሰገደት ውስተ ምድር ወትቤሎ እመ ረከብኩ ሞገሰ በቅድመ አዕይንቲከ ሁቀኒ እስመ እንግዳ አነ ።

፲፩ ወአውሥኦ ብኤዝ ወይቤላ ዜና ዜነውኒ ኵሎ ዘገበርኪ ምስለ ሐማትኪ እምኅረ ሞተ ምትኪ ወእፎ ኀደጊ አባኪ ወእመኪ ወብሔረ ሙላድኪ ወመጻእኪ ኀበ ሕዝብ ዘኢታእምሪ ትካት ።

፲፪ ወይዕሢኪ እግዚአብሔር በከመ ገበርኪ ወይኩን ዕሤትኪ ፍጹመ በኀበ እግዚአብሔር አምላከ እስራኤል ዘመጻእኪ ኀቤሁ ከመ ትትአመኒ በክነፊሁ ።

፲፫ ወትቤሎ ሩት ረከብኩ ሞገሰ በቅድመ አዕይንቲከ እስመ አስተፍሣሕከኒ ወናዘዝከሁ ለልበ አመትከ ወናሁ አነ እከውንከ ከመ አሐቲ እምነ እእማቲከ ።

፲፬ ወይቤላ ብኤዝ ሶበ ኮነ ጊዜ ምሳሕ ንዒ ዝየ ወብልዒ ኅብስተ ወትጸብሒ ኅብስተኪ በብሒእ ወነበረት ሩት እመንገለ ገቦሆሙ ለእለ የዐፅዱ ወአስተጋብአ ላቲ ብኤዝ ጥሕነ ወበልዐት ወጸግበት ወአትረፈት ።

፲፭ ወተንሥአት ትትቀረም ወአዘዞሙ ብኤዝ ለደቁ ወይቤሎሙ ለትእሪ ማእከለ ከላስስት ወኢታስተኀፍርዋ ።

፲፮ ወሁሩ ላቲ እምዘአስተጋብአት ወኅድጉ ላቲ ወትብላዕ ወትእሪ ወኢትገሥፅዋ ።

፲፯ ወአረየት እምገራህት እስከ መስየ ወዘበጠቶ ለዝክቱ ዘአስተጋብአት ወኮነ ሰገሙ በመስፈርተ ኢፍ ።

፲፰ ወነሥአት ወአተወት ሀገረ ወርእየት ሐማታ ዘአረየት ወአምጽአት ሩት ወወሀበታ ዘአትረፈት እምድኅረ ጸግበት ።

፲፱ ወትቤላ ሐማታ በአይቴ አረይኪ ዮም ወበአይቴ ገበርኪ ቡሩክ ለይኩን ዘአእመረኪ፡ ወአይድዐታ ሩት ለሐማታ በአይቴ ገብረት ወነገረታ ስሞ ለውእቱ ብእሲ ዘኀቤሁ ወዓልኩ ዮም ብኤዝ ውእቱ ።

፳ ወትቤላ ኑኃሚን ለመርዓታ ቡሩክ ውእቱ እግዚአብሔር እስመ ኢኀደገ ምሕረቶ ምስለ ሕያዋን ወምስለ ምውታን ወትቤላ ኑኃሚን ብእሲሁሰ ቅሩብነ ውእቱ እምእለ ይትሐመዉነ ።

፳፩ ወትቤላ ሩት ለሐማታ እስመ ይቤለኒ ምስለ አዋልድየ ትልዊ እስከ የኀልቅ ማእረርነ ።

፳፪ ወትቤላ ኑኃሚን ለሩት መርዓታ ሠናይ ወለትየ ሰበ ትተልዊ አዋልዲሁ ወኢይረክቡኪ ውስተ ገራህተ ባዕድ ።

እሷም ከአጫጆቹ በኋላ ከነዶው የወደቀውን እንድ ቃርምና እንድለቅም ብላ መጣች ከጧት እስከ አሁን ቆማ ለች፡ ከእርሻውም ጥቂት ስንኳ አልተወችም አለው ።

በአስም ሩትን መውረስ እንዲገባኝ አላወቅሽምን ልጄ ሆይ! ለመቃረም ወደ ባዕድ እዝመራ አትግቢ፡ ከዚህም አትሂጂ ልጆቼን ተከተያቸው ።

ወደ ሚያጭዱት አዝመራ ተመልከቺ የሚነካሽ ሰው እንዳይኖር እነሆ ልጆቼን አዝዝልሻለሁ ተከተያቸው ውኃም ብትጠሚ ከዕቃው ዘንድ ሂደሽ ልጆች ከመጡት ውኃ ጠጪ አላት ።

በግንባሯ ተደፍታ ሰገደችለት፡ በፊትህ ባለሟልነትን አግኝቼ እንደሆነ እንግዳ ነኝና ዕወቀኝ አለቻው ።
፩ ሳሙ፡ ፳፭ ፳፫ - ፵፩ ።

በአስም ባልሽ ከሞተ በኋላ ለአማትሽ ያሠራሽውን ሥራ ሁሉ ነግረዉኛል እናትና አባትሽን የተወለድሽበት አገርሽን ትተሽ ቀድሞ ወደ ማታውቂው ወገን እንደምን መጣሽ፤ ብሎ መለሰላት ።

ለአማትሽ በጎ ነገርን እንዳደረግሽ እግዚአብሔር ዋጋ ሽን ይስጥሽ፡ በክንፈ ረድኤቱም አምነሽ ወደሱ በመጣሽበት በእስራኤል ፈጣሪ በእግዚአብሔር ዘንድ ዋጋሽ ፍጹም ይሁን አላት ። ፩ ሳሙ፡ ፳፬ ፲፱ ።

ሩትም ደስ አሰኝተሽኛልና የኔን የባርያህንም ልብ አረጋግተኸዋልና በፊትህ ባለሟልነትን አገኘሁ፡ እነሆ እኔም ከባሮችህ እንደ አንዲቱ ባሪያ እሆንኻለሁ አለችው ።

በአስም በምሳ ጊዜ ወደዚህ መጥተሽ እንጀራን ብዪ እንጀራሽንም በመጣጣው አጥልቂ አላት፡ ሩትም በሚያጭዱት ሰዎች ጐን ተቀመጠች በአስም በሶውን ሰበሰበላት በልታና ጠግባም አተረፈች ። ዘኍ፡ ፯ ፫ ።

ትቃርም ዘንድ ተነሣች፡ በአስም አሽከሮቹን በነዶው መካከል ትልቀም አትከልክሏት አላቸው ።

የሰበሰበችውንም እንሥታችሁ አሽክሚት፡ ለቅማ ትብላ አትቈጧት ብሎ አዘዛቸው ።

እስኪመሽም ድረስ ከእርሻው ለቀመች፡ የለቀመችውንም ያን ገብስ ወቅታው ዓሥር ላዳን ሆነ ።

ይህን ይዛ ወደ ከተማ ገባች፡ አማቷም የለቀመችውን አየች፡ ሩትም ከጠገበች በኋላ ያተረፈችው አውጥታ ሰጠቻት ። ሩት ፪ ፲፬ ።

አማቷም ዛሬ ወዴት ለቀምሽ፤ ወዴትስ ሰትሠሪ ዋልሽ፤ በፍቅር ያወቀሽ ሰው የተባረከ ይሁን አለቻት፡ ሩትም ለአማቷ ወዴት ስትሠራ እንደዋለች ነገረቻትና ዛሬ የዋልኩበት የዚያንም ሰው ስም ብኦስ ይባላል ብላ ነገረቻት ።

ኑኃሚንም ምራቷን ለሞቱትና ላሉት ቸርነቱን አልተወምና እግዚአብሔር ክቡር ምስጉን ነው አለቻት፡ ኑኃሚን ሰውዬው ግን ከሚወርሱን ወገን አቅራቢያችን ነው አለቻት ። ዘፍ፡ ፲፬ ፲፱ ። ሩት ፫ ፲ ።

ሩትም አማቷን አዝመራችን እስኪያልቅ ድረስ ልጆቹን ተከተይ ብሎኛልና ልጆቹን እከተላለሁ አለቻት ።

ኑኃሚንም ምራቷ ሩትን ልጄ! ልጆቹን ብትከተዪ መልካም ነው ነገር ግን በሌላ ሰው እርሻ አያግኙሽ አለቻት።

፳፫ ወተለውቶን ሩት ለአዋልደ ቦኤዝ ከመ ትእረ እስከ አመ የኀልቅ ማእረረ ሰገም ወሥርናይ ወነበረት ምስለ ሐማታ ።

## ምዕራፍ ፫ ።

፩ ወትቤላ ኑኃሚን ለሩት መርዓታ ወለትየ ኢየኃሥሥኑ ለኪ ዕረፍተ ከመ ትሠኒ ላዕሌኪ ።

፪ ወይእዜኒ አኮኑ ቦኤዝ ማእምርነ ዘምስለ አዋልዲሁ ሀሎኪ ናሁ ውእቱ ይገብር ውስተ ዐውደ እክሉ ዮም በዛቲ ሌሊት ።

፫ ወአንቲሰ ተሐፀቢ ወተቀብኢ ወተላበሲ አልባሲኪ ወሑሪ ኀበ ዐውደ እክሉ ወኢልብ ሰብእ ዘይሬእየኪ እስከ የኀልቅ በሊዐ ወሰትዮ ።

፬ ወሶበ ሰከበ አእምሪ መካኖ ኀበ ኖመ ወህየ ሑሪ ወከሥቲ ኀበ እገሪሁ ወሰከቢ ወውእቱ ለሊሁ ይኤዝዘኪ ዘከመ ትገብሪ ።

፭ ወትቤላ ሩት ኵሎ ዘከመ ትቤልኒ እገብር ።

፮ ወሖረት ኀበ ዐውደ እክል ወገብረት ኵሎ ዘከመ አዘዘታ ሐማታ ።

፯ ወበልዐ ወሰትየ ቦኤዝ ወተፈሥሐ ልቡ ወሖረ ወሰከበ ኀበ ክምር ወመጽአት ድሚተ ወከሠተት ኀበ እገሪሁ ወሰ ከበት ።

፰ ወመንፈቀ ሌሊት ከዊኖ ነቅሐ ቦኤዝ ወደንገፀ ወረከበ ብእሲተ ኀበ እገሪሁ ።

፱ ወይቤላ መኑ አንቲ ወትቤሎ አነ ሩት አመትከ ወከ ድነኒ ጽንፈ ልብስከ እስመ መስተሐምም አንተ ።

፲ ወይቤላ ቡርክት አንቲ ለእግዚአብሔር ወለትየ እስመ ኄየስት ምሕረት ደኃሪት እምቀዳሚትኪ ዘኢሖርኪ ወኢተለውኪ ወራዙተ ነዳያነ ወአብዕልተ ።

፲፩ ወይእዜኒ ወለትየ ኢትፍርሂ ኵሎ ዘትቤልኒ እገብር ለኪ ወየአምር ኵሉ ነገደ ሕዝብየ ከመ ብእሲተ ኃይል አንቲ ፡ ወከመ መስተሐምም ወበሕቱ ቦ መስተሐምም ዘይቀርብ እምኔየ ።

፲፪ ቢቲ ዛተ ሌሊተ ወሶበ ጸብሐ ለእመ ተሐመወ ሠናይ ውእቱ ለይትሐመውኪ ፡ ወለእመሰ ኢፈቀደ ይትሐሞ ው እቱ ሕያው እግዚአብሔር ከመ አነ እትሐመውኪ ወቢቲ እስከ ይጸብሕ ።

፲፫ ወቤተት ኀበ እገሪሁ እስከ ይጸብሕ ወተንሥአት እን በለ ይትረአይ ሰብእ ።

፲፬ ወይቤ ቦኤዝ አልቦ ዘየአምር ከመ መጽአት ብእሲት ኀበ ዐውደ እክል ።

፲፭ ወይቤላ አምጽኢ ልብሰ ዘላዕሌኪ ወአኀዘ ወሰፈረ ውስቴቱ ስድስ እክለ ሰገም ወአፆራ ወቦአት ውስተ ሀገር ።

፲፮ ወአተወት ሩት ኀበ ሐማታ ወትቤላ ምንት ዝንቱ ወለ ትየ ፡ ወአይድዐታ ኵሎ ዘከመ ገብረ ላቲ ውእቱ ብእሲ ።

፲፯ ወትቤላ እላንተ ስድሰ እክለ ሰገም ወሀበኒ ወይቤለኒ ኢትእትዊ ዕራቀኪ ኀበ ሐማትኪ ።

፳፫ ሩትም የሥንዴውና የገብሱ አዝመራ እስኪያልቅ ድ ረስ የቦኤዝን ልጆች ተከተለቻቸው ከአማቷም ጋር ኖረች።

## ምዕራፍ ፫ ።

፩ ኑኃሚን ምራቷ ሩትን ልጄ በጎ ነገር ትደረግልሽ ዘንድ እኔስ ላንቺ ዕረፍትን አልፈልግልሽምን፤ አለቻት ።

፪ አሁንም ከልጆቹ ጋራ ያልሽበት ቦኤዝ በመውረስ የሚ ያውቀን አይደለምን፤ እነሆ እሱ ዛሬ በዚች ሌሊት ዓው ድማ ይጥላል ።

፫ አንቺ ግን ገላሽን ታጥበሽ ሽቱ ተቀብ፤ሽ ልብስሽን ለብሰሽ ወደ አኽሉ ዓውድማ ሂጂ መብሉ መጠጡ እስኪ ፈጸም ድረስ የሚያይሽ ሰው አይኑር ። ፪ ሳሙ ፡ ፲፱ ፪ ።

፬ በተኛ ጊዜ የተኛበት ስታውን ዐውቀሽ ወደዚያ ሂጂ ከእግሩም ዘንድ ገልጠሽ ተኚ፤ የምታደርጊውንም እሱ ያዝሽል ።

፭ ሩትም ያልሽኝን ሁሉ አደርጋለሁ አለቻት ።

፮ ወደ አኽሉም ዓውድማ ሂዳ አማቷ ያዘዘቻትን ሁሉ አደረገች ።

፯ ቦኤዝም በልቶ ጠጥቶ ልቡናውን ደስ ብሎት ከክምሩ ዘንድ ተኛ (እሷም) ቀስ ብላ መጥታ ከእግሩ ዘንድ ገልጣ ተኛች ። መሳ፡ ፲፱ ፮ ፡ ፪ ሳ፩ ።

፰ እኩለ ሌሊት በሆነ ጊዜ ቦኤዝ ነቃ ደነገጠ ፡ ከእግሩ ዘንድ ሴት አገኘ ። መሳ፡ ፲፯ ፳፱ ። ኢዮብ ፯ ፲፫ ።

፱ አንቺ ማነሽ፤ አላት ፡ እኔ ባርያህ ሩት ነኝ ፡ አንተ እኔን መውረስ የሚገባህ ነህና የልብስህን ጫፍ አልብሰኝ አለችው ። ዘዳ፡ ፳፪ ፴ ። ሩት ፫ ፲ ።

፲ ቦኤዝም ድኾች ጐልማሶችንና ገንዘብ ያላቸው ባለጸ ጎችን ተከትለሽ ያልሄድሽ ከቀድሞው በጎነትሽ የዛሬው በጎነትሽ በልጧልና ልጄ፤ አንቺ ለእግዚአብሔር የተባረ ክሽ ነሽ አላት ። ሩት ፪ ፳ ፡ ፩ ፰ ።

፲፩ ልጄ አትፍሪ ያልሽኝን ሁሉ አደርግልሻለሁ ፡ አን ቺ የወገኖቼ ሚስት እንደሆንሽ እኔም መውረስ የሚገ ባኝ እንደሆንኩ የወገኖቼ ወገን ሁሉ ያውቃል ነገር ግን ከኔ የሚቀርብ መውረስ የሚገባው አለ፤ አላት ።

፲፪ ዛሬ ሌሊት እደሪ ፡ ከነጋ በኋላ ያ ሰውዬ ቢወርስሽ ደግ ነው ፡ ባይወድ ግን እኔ እንድወርስሽ እግዚአብሔር ሕያው ነው ፡ እስኪነጋ ድረስ እደሪ አላት ።
ዘዳ፡ ፳፭ ፭ ። መሳ፡ ፰ ፲፱ ፡ ፩ ሳሙ፡ ፳፭ ፳፮ ።

፲፫ እስኪነጋም ድረስ ከእግሩ ዘንድ አደረች ፡ ሰው ሳይ ተያይ ተነሣች ።

፲፬ ቦኤዝም ወደ አኽሉ ዓውድማ ሴት እንደመጣች ሰው ዐይወቅ አለ ። ዘዳ፡ ፳፭ ፭ ።

፲፭ የለበስሽውን ልብስ አምጪ ብሎ ይዞ ስድስት ላዳን ገብስ ሰፍሮ በልብሷ ቋጥሮ አሸከማት ፡ ወደ አገርም ገባች ።

፲፮ ሩትም ወደ አማቷ ገባች ፡ ልጄ፤ ይህ ምንድር ነው፤ አለቻት ፡ እሷም ያ ሰው ያደረገላትን ሁሉ ነገረቻት ።

፲፯ ይህን ስድስት ላዳን ገብስ ሰጠኝ ፡ ወደ አማትሽም ባዶሽን አትመለሺ አለኝ አለቻት ።

፲፰ ወትቤላ ንበሪ ወለትየ እስከ ትሬእዪ ከመ ኢይወድቅ ቃልየ እስመ ኢያረምም ውእቱ ብእሲ ወኢየሀድእ ዮም እስከ ይገብር ለዝንቱ ነገር ።

ያ ሰው ዝም አይልምና ይህንንም ነገር እስኪያደርገው ድረስ ዛሬ አያርፍምና ቃሌ እንዳይቀር እስክታዪ ድረስ ልጄ ተቀመጪ አለቻት ። መዝ፡ ፴፯ ፭ ።

## ምዕራፍ ፬ ።

፩ ወዐርገ ቦኤዝ ኆኅተ አንቀጽ ወነበረ ሀየ ወመጽአ ዝክቱ መስተሐምው ዘይቤ ቦኤዝ ይኅልፍ ወይቤሎ ቦኤዝ ግኀሥ ወንበር ዝየ እስከ ንትናገር ወግኀሠ ወነበረ ።

ቦኤዝ ወደ ሸንጎ ወጥቶ በዚያ ተቀመጠ ፡ ቦኤዝ ያገባ ያለው ያ ሰው አልፎ ይሄድ ዘንድ መጣ ፡ ቦኤዝም እገሌ ንነጋገር ድረስ ገብተህ በዚህ ተቀመጥ አለው እሱም ገብቶ ተቀመጠ ።

፪ ወነሥአ ቦኤዝ ዐሠርተ ዕደወ እምሊቃናተ ሀገር ወይቤሎሙ ንበሩ ዝየ ወነበሩ ።

ቦኤዝም ከአገር ሽማግሌዎች ዓሥር ሰዎች አምጥቶ በዚህ ተቀመጡ አላቸው ፡ ተቀመጡም ። ፩ ነገ፡ ፳፩ ፰ ።

፫ ወይቤሎ ቦኤዝ ለመስተሐምው መክፈልተ ገራህት ዘእኁነ አቤሜሌክ አግብእ ላቲ ለኑኃሚን እንተ አተወት እምሐቅለ ሞአብ ።

ቦኤዝ መውረስ የሚገባውን ሰው የወንድማችንን የአቤሜሌክን ዕጣ ከሞዓብ አውራጃ ለተመለሰች ለኑኃሚን መልስላት አለው ።

፬ ወአንሰ ነገርኩከ ትስማዕ እንዘ እብል ኅረይ ለከ በቅድመ እለ ይነብሩ ወበቅድመ ሊቃናት ወበቅድመ ሕዝብ እመሰ ትትሐመው ተሐመው ፡ ወእመሰ ኢትትሐመው አይድዐኒ ወአአምር እስመ ዘይቀድምከ ተሐምዎ አንተ ወአነ እምድኅሬከ ፡ ወይቤሎ አነ ውእቱ መስተሐምው ።

እኔ ትሰማኝ ዘንድ በሸንጎ በተቀመጡ በአለቆችና በሕዝቡም ፊት የሚሻልህን ምረጥ ብዬ ነገርኩህ አስቀድሞ መውረስ የሚገባህ አንተ ነህና እኔ ግን ካንተ በኋላ ነኝና ትወርስ እንደሆ ንገረኝ ልወቅ የምወርሰው እኔ ነኝ አለው ፡ እሱም ወራሹ እኔ ነኝ ፤ አለው ።

፭ ወይቤሎ ቦኤዝ ከመ ትሣእክ ገራህተ እምእደ ኑኃሚን ወእምነ ሩት ሞአባዊት ብእሲቱ ለዘሞተ ወኪያሃኒ ርቱዕ ትንሣእ ከመ ታቅም ስሞ ለዘሞተ ላዕለ ርስቱ ።

ቦኤዝም ከኑኃሚን እጅ ከሟቹ ሚስት ከሞዓብ ሴት ከሩት እጅ እርሻውን እጅ እንዳደረግህ (እህንም) እሷን አግብተህ የሟቹን ስም በርስቱ ላይ ልታስጠራው ይገባል አለው ። ዘዳ፡ ፳፭ ፭ ። ሩት ፩ ፲ ።

፮ ወይቤ መስተሐምው ኢይክል ተሐምዎ ከመ ኢይኅጕል ርስትየ ተሐሞ ለርእስከ ተሐምዎ ዘዚአየ እስመ ኢይክል ተሐምዎ ።

ያም መውረስ የሚገባው ሰው ርስቴን እንዳላጣ መውረስ አይቻለኝም አለ ፡ መውረስ አይቻለኝምና የኔን እወራረስ አንተ ለራስህ ውረስ አለው ። ሩት ፫ ፲፫ ።

፯ ወከመዝ ውእቱ ሕጎሙ ለተሐምዎ በቅድመ እስራኤል ወበእንተ ተዋልጦ ከመ ያቅም ቃሎ ወይፈትሕ ውእቱ ብእሲ ሣእኖ ወይሁብ ለካልኡ ዘይትሐመው ተሐምዎ ዚአሁ ወከመዝ ውእቱ ስምዑ በውስተ እስራኤል ።

በእስራኤል ዘንድ የአወራረስ ሥርዓቱ (ፍርዱ) እንዲህ ነው ፡ አወራረስን ስለ መለዋወጥ ቃሉን ያጠና ዘንድ ፍርዱ እንደዚህ ነው ፡ የሱን እወራረስ ለሚወርስ ወንድሙ ጫማውን አውልቆ ይሰጠዋል ፡ በእስራኤል ዘንድ ምስክሩ እንዲህ ነው ። ዘሌ፡ ፳፯ ፲፫ ። ዘዳ፡ ፳፭ ፯ ።

፰ ወይቤሎ መስተሐምው ለቦኤዝ ንሣእ ለከ ተሐምዎ ዘዚአየ ወፈትሐ ሣእኖ ወወሀበ ።

መውረስ የሚገባው ሰው ቦኤዝን የኔን ውርስ ላንተ ውረሰው ብሎ ጫማውን አውልቆ ሰጠው ።

፱ ወይቤሎሙ ቦኤዝ ለሊቃናት ወለኵሉ ሕዝብ ስምዑ አንትሙ ዮም ከመ ነሣእኩ ኵሎ ዘአቤሜሌክ ወኵሎ ንዋዮሙ ለኬሌዎን ወለመሐሎን እምእዴሃ ለኑኃሚን ።

ቦኤዝም (ቦኤዝ) ወገኖቹን ሁሉና አለቆችን የኬሌዎንና የመሐሎን ገንዘብ ሁሉና የአቤሜሌክን ገንዘብ ሁሉ ከኑኃሚን እጅ እንደወሰድኩ ።

፲ ወለሩት ሞአባዊት ብእሲተ መሐሎን ነሣእክዋ ሊተ ትኩነኒ ብእሲተ ወከመ አቅም ስሞ ለዘሞተ ላዕለ ርስቱ ወኢይጠፋእ ስሙ እምአኀዊሁ ወእምነገደ ሕዝቡ ስምዐ አንትሙ ዮም ።

የሞዓብ ሴት ከምትሆን የመሐሎን ሚስት ሩትንም ሚስት ትሆነኝ ዘንድ የሟቹንም ስም በርስቱ ላይ አስጠራው ዘንድ ከወገኑ ነገድና ከወንድሞቹ ተለይቶ ስሙ እንዳይጠፋ እንዳገባኋት ዛሬ እናንተ ምስክሮቼ ናችሁ አላቸው ። ዘዳ ፳፭ ፮ ፡ ዘሩት ፪ ፩ ።

፲፩ ወይቤሉ ኵሉ ሕዝብ በኆኅተ አንቀጽ ስምዐ ንሕነ ፡ ወሊቃናትኒ ይቤልዎ ይረስያ ለከ እግዚአብሔር ለብእሲትከ እንተ ትበውእ ውስተ ቤትከ ከመ ራሔል ወከመ ልያ እለ ሐነጸዉ ለቤተ እስራኤል ክልኤሆን ፡ ወግበር ኀይለ ውስተ ኤፍራታ ወይኩንከ ስም በውስተ ቤተ ልሔም ።

በሸንጎም ያሉ ሕዝብ ሁሉ ምስክሮችህ ነን አሉት ፡ ሽማግሌዎችም ወደ ቤትህ የምትገባ ሚስትህን እግዚአብሔር ላንተ የያዕቆብን ቤት እንዳነፁት እንደ ራሔልና እንደ ልያ ያድርጋት በኤፍራታም ኃይልን አድርግ በቤተ ልሔምም ስም የሚያስጠራ ልጅ ይስጥህ አሉት ።

፲፪ ወይኩን ቤትከ ከመ ቤተ ፋሬስ ዘወለደት ትእማር ለይሁዳ ወዘርአ የሀብከ እግዚአብሔር በላዕለ ዛቲ ወለት ።

ወገንህም ለይሁዳ እንደወለደችለት እንደ ፋሬስ ወገን ይሁን እግዚአብሔር ከዚች ልጅ ዘር ይስጥህ አሉት ።

ወነሥኣ ቦኤዝ ለሩት ወኮነቶ ብእሲተ ወወሀቦ እግዚአብሔር ወፀንሰት ወወለደት ወልደ። ፲፫ ቦአዝም ሩትን አገባት ሚስትም ሆነችው፤ እግዚአብሔርም ዘር ሰጣት ፀንሳም ወንድ ልጅ ወለደች።

ወይቤላ አንስት ለኑኃሚን ይትባረክ እግዚአብሔር ዘኢያኅጥአኪ ዮም መስተሐምመ በዘይሰመይ ስምኪ በውስተ እስራኤል። ፲፬ ሴቶችም ኑኃሚንን በእስራኤል ስምሽ በሚጠራ ጊን ዘብ ዛሬ ወራሽ ያላሳጣሽ እግዚአብሔር ይክበር ይመስገን አሏት። ማቴ፡ ፩ ፭። ሉቃ፡ ፩ ፶፰።

ወይከውንኪ በዘታገብኢ ነፍሰኪ ወዘየሐስና ለሊበትኪ እስመ አፍቀረተኪ መርዓትኪ እንተ ወለደት ዘይኄይሰኪ ለኪ እምሰብዐቱ ደቂቅ። ፲፭ ልቡናሽን ወደ ደስታ በምትመልሺ ገንዘብ የምትመልሺበት ይሆንሻል፤ ከሰባት ልጅ የሚበልጥ የወለደችልሽ ምራትሽ ወዳሻለችና ያረጀ ሰውነትሽን የሚያድስልሽ ይሆንሻል። ዘፍ፡ ፵፯ ፲፪። ፩ ሳሙ፡ ፩ ፰።

ወነሥአቶ ኑኃሚን ለውእቱ ሕፃን ወአንበረቶ ውስተ ሕፅና ወኮነቶ ሐፃኒተ። ፲፮ ኑኃሚንም ያንን ልጅ ተቀብላ በክንዷ ታቀፈችው ሞግዚትም ሆነችው።

ወሰመያሁ አግዋሪያ ስሞ እንዘ ይብላ እስመ ተወልደ ወልድ ለኑኃሚን ወሰመዩ ስሞ ኢዮቤድ ወውእቱ አቡሁ ለእሴይ አቡ ዳዊት። ፲፯ ጐረቤቶቿም ለኑኃሚን ልጅ ስለ ተወለደላት ዕዘንን የሚያስረሳ ሲሉ ስሙንም ኢዮቤድ አሉት፤ ይኸውም የዳዊት አያት የዕሤይ አባት ነው። ዘፍ፡ ፶ ፳፫። ሉቃ፡ ፩ ፶፱።

ወከመዝ ውእቱ ትውልዱ ለፋሬስ፤ ፋሬስ ወለዶ ለኤስሮም። ፲፰ የፋሬስም ትውልዱ እንዲህ ነው፤ ፋሬስ ኤስሮምን ወለደው።

ወኤስሮም ወለዶ ለአራም፤ ወአራም ወለዶ ለአሚናዳብ። ፲፱ ኤስሮምም አራምን ወለደው፤ አራምም አሚናዳብን ወለደው። ፩ ዜና መ፡ ፪ ፲፩።

ወአሚናዳብ ወለዶ ለነአሶን፤ ወነአሶን ወለዶ ለሰልሞን። ፳ አሚናዳብም ነአሶንን ወለደው፤ ነአሶንም ሰልሞንን ወለደው። ዘፀ፡ ፮ ፳፫።

ወሰልሞን ወለዶ ለቦኤዝ፤ ወቦኤዝ ወለዶ ለኢዮቤድ። ፳፩ ሰልሞንም ቦአስን (ቡኤዝን) ወለደው፤ ቦአዝም ኢዮቤድን ወለደው። ዘኁ፡ ፩ ፯።

ወኢዮቤድ ወለዶ ለእሴይ፤ ወእሴይ ወለዶ ለዳዊት። ፳፪ ኢዮቤድም እሤይን ወለደው እሤይም ዳዊትን ወለደው።

ተፈጸመ አሬት ዘሩት፤
ወስብሐት ለእግዚአብሔር ፈጻሚ ተድናሰን ለዕቤሬት፤
አሜን።

ለዘለዓለሙ ለእግዚአብሔር ክብር ምስጋና ይግባውና፤
የሩትን ዜና የሚናገር መጽሐፍ ደረሰ ተፈጸመ።
አሜን።

እንጂ ፡ ወደ ፡ እነዚያ ፡ ሰራዊት ፡ እመራሃለኹ ፡ አለ ።

16 ፤ ወደ ፡ ታችም ፡ እንዲወርድ ፡ ባደረገው ፡ ጊዜ ፥ እንሆ ፥ ከፍልስጥኤማውያንና ፡ ከይሁዳ ፡ ምድር ፡ ከወሰዱት ፡
ከብዙ ፡ ምርኮ ፡ ኹሉ ፡ የተነሣ ፡ በልተው ፡ ጠጥተውም ፡ የበዓልም ፡ ቀን ፡ አድርገው ፡ በምድር ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፡ ተበትነው ፡
ነበር ።

17 ፤ ዳዊትም ፡ ከማታ ፡ ዠምሮ ፡ እስከ ፡ ማግስቱ ፡ ማታ ፡ ድረስ ፡ መታቸው ፤ ከነርሱም ፡ በግመል ፡ ተቀምጠው ፡
ከሸሹ ፡ ከአራት ፡ መቶ ፡ ጕልማሳዎች ፡ በቀር ፡ አንድ ፡ ያመለጠ ፡ የለም ።

18 ፤ ዳዊትም ፡ ዐማሌቃውያን ፡ የወሰዱትን ፡ ኹሉ ፡ አስጣላቸው ፥ ኹለቱንም ፡ ሚስቶቹን ፡ አዳነ ።

19 ፤ ከወንዶችና ፡ ከሴቶች ፡ ልጆች ፥ ከወሰዱትም ፡ ምርኮ ፡ ኹሉ ፥ ታላቅም ፡ ኾነ ፡ ታናሽም ፡ ኾነ ፥ ምንም ፡
የጐደለባቸው ፡ የለም ፤ ዳዊትም ፡ ኹሉን ፡ አስጣለ ።

20 ፤ ዳዊትም ፡ የበጉንና ፡ የላሙን ፡ መንጋ ፡ ኹሉ ፡ ወሰደ ፥ ከራሱም ፡ ከብት ፡ ፊት ፡ እየነዳ ፡— ይህ ፡ የዳዊት ፡ ምርኮ ፡
ነው ፡ አለ ።

21 ፤ ዳዊትም ፡ ደክመው ፡ ዳዊትን ፡ ይከተሉት ፡ ዘንድ ፡ ወዳልቻሉ ፥ በቦሦር ፡ ወንዝ ፡ ወዳስቀራቸው ፡ ወደ ፡ ኹለቱ ፡
መቶ ፡ ሰዎች ፡ መጣ ፤ እነርሱም ፡ ዳዊትን ፡ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ የነበሩትን ፡ ሕዝብ ፡ ሊቀበሉ ፡ ወጡ ፤ ዳዊትም ፡ ወደ ፡
ሕዝቡ ፡ በቀረበ ፡ ጊዜ ፡ ደኅንነታቸውን ፡ ጠየቀ ።

22 ፤ ከዳዊትም ፡ ጋራ ፡ ከኼዱ ፡ ሰዎች ፡ ክፉዎቹና ፡ ምናምንቴዎቹ ፡ ኹሉ ፡— እነዚህ ፡ ከእኛ ፡ ጋራ ፡ አልመጡምና ፡
እየራሳቸው ፡ ሚስቶቻቸውንና ፡ ልጆቻቸውን ፡ ይዘው ፡ ይኺዱ ፡ እንጂ ፡ ካስጣልነው ፡ ምርኮ ፡ ምንም ፡ አንሰጣቸውም ፡
አሉ ።

23 ፤ ዳዊትም ፡— ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፥ የጠበቀን ፡ በእኛም ፡ ላይ ፡ የመጣውን ፡ ጭፍራ ፡ በእጃችን ፡ አሳልፎ ፡ የሰጠን ፡
እግዚአብሔር ፡ በሰጠን ፡ ነገር ፡ እንዲህ ፡ አታድርጉ ፤

24 ፤ ይህንስ ፡ ነገ ፡ ማን ፡ ይሰማችኋል ፥ ነገር ፡ ግን ፡ የተዋጉትና ፡ ዕቃውን ፡ የጠበቁት ፡ ዕድል ፡ ፈንታ ፡ እኩል ፡
ይኾናል ፥ አንድነት ፡ ይካፈላሉ ፡ አለ ።

25 ፤ ከዚያም ፡ ቀን ፡ ዠምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ይህን ፡ ለእስራኤል ፡ ሥርዐትና ፡ ፍርድ ፡ አደረገው ።

26 ፤ ዳዊትም ፡ ወደ ፡ ጺቅላግ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ለዘመዶቹ ፡ ለይሁዳ ፡ ሽማግሌዎች ፡— እንሆ ፥ ከእግዚአብሔር ፡
ጠላቶች ፡ ምርኮ ፡ በረከትን ፡ ተቀበሉ ፡ ብሎ ፡ ከምርኮው ፡ ሰደደላቸው ።

27 ፤ በቤቴል ፡ ለነበሩ ፥ በራሞት ፡ በደቡብ ፡ ለነበሩ ፡

28 ፤ በየቲር ፡ ለነበሩ ፥ በዐሮዔር ፡ ለነበሩ ፥ በሢፍሞት ፡ ለነበሩ ፥ በኤሽትሞዐ ፡ ለነበሩ ፥

29 ፤ በቀርሜሎስ ፡ ለነበሩ ፥ በይረሕምኤላውያንና ፡ በቄናውያን ፡ ከተማዎችም ፡ ለነበሩ ፥

30 ፤ በሔርማ ፡ ለነበሩ ፥ በቦራሣን ፡ ለነበሩ ፥ በዓታክ ፡ ለነበሩ ፥ በኬብሮን ፡ ለነበሩ ፥

31 ፤ ዳዊትና ፡ ሰዎቹም ፡ በተመላለሱበት ፡ ስፍራ ፡ ለነበሩ ፡ ሰዎች ፡ ኹሉ ፡ ላከ ።

________________መጽሐፈ ፡ ሳሙኤል ፡ ቀዳማዊ ፥ ምዕራፍ ፡ 31 ። ________________

ምዕራፍ ፡ 31 ።

1 ፤ ፍልስጥኤማውያንም ፡ ከእስራኤል ፡ ጋራ ፡ ተዋጉ ፤ የእስራኤልም ፡ ሰዎች ፡ ከፍልስጥኤማውያን ፡ ፊት ፡
ሸሹ ፥ ተወግተውም ፡ በጊልቦዓ ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ወደቁ ።

2 ፤ ፍልስጥኤማውያንም ፡ ሳኦልንና ፡ ልጆቹን ፡ በእግር ፡ በእግራቸው ፡ ተከትለው ፡ አባረሯቸው ፤ ፍልስጥኤማውያንም ፡
የሳኦልን ፡ ልጆች ፡ ዮናታንንና ፡ ዐሚናዳብን ፡ ሜልኪሳንም ፡ ገደሉ ።

3 ፤ ሰልፍም ፡ በሳኦል ፡ ላይ ፡ ጠነከረ ፥ ቀስተኛዎችም ፡ አገኙት ፤ ርሱም ፡ ከቀስተኛዎቹ ፡ የተነሣ ፡ እጅግ ፡ ተጨነቀ ።

4 ፤ ሳኦልም ፡ ጋሻ ፡ ዣግሬውን ፡— እነዚህ ፡ ቈላፋን ፡ መጥተው ፡ እንዳይወጉኝና ፡ እንዳይሣለቁብኝ ፡ ሰይፍኽን ፡

መዘኸ ፡ ውጋኝ ፡ አለው ። ጋሻ ፡ ጃግሬው ፡ ግን ፡ እጅግ ፡ ፈርቶ ፡ ነበርና ፤ እንቢ ፡ አለ ። ሳኦልም ፡ ሰይፉን ፡ ወስዶ ፡ በላዩ ፡ ወደቀ ።

5 ፤ ጋሻ ፡ ጃግሬውም ፡ ሳኦል ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ርሱ ፡ ደግሞ ፡ በሰይፉ ፡ ላይ ፡ ወደቀ ፤ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ ሞተ ።

6 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ ሳኦል ፡ ሦስቱም ፡ ልጆቹ ፡ ጋሻ ፡ ጃግሬውም ፡ ሰዎቹም ፡ ኹሉ ፡ ባንድ ፡ ላይ ፡ ሞቱ ።

7 ፤ በሸለቆውም ፡ ማዶና ፡ በዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ የነበሩ ፡ እስራኤላውያን ፡ የእስራኤል ፡ ሰዎች ፡ እንደ ፡ ሸሹ ፤ ሳኦልና ፡
ልጆቹም ፡ እንደ ፡ ሞቱ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ ከተማዎቹን ፡ ለቅው ፡ ሸሹ ፤ ፍልስጥኤማውያንም ፡ መጥተው ፡ ተቀመጡባቸው ።

8 ፤ በማግስቱም ፡ ፍልስጥኤማውያን ፡ የሞቱትን ፡ ለመግፈፍ ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ ሳኦልና ፡ ሦስቱ ፡ ልጆቹ ፡ በጊልቦዓ ፡
ተራራ ፡ ላይ ፡ ወድቀው ፡ አገኟቸው ።

9 ፤ የሳኦልንም ፡ ራስ ፡ ቈረጠው ፡ የጦር ፡ ዕቃውን ፡ ገፈው ፡ ለጣዖታቱ ፡ መቅደስ ፡ ለሕዝቡም ፡ የምሥራች ፡ ይሰጥ ፡
ዘንድ ፡ ወደፍልስጥኤማውያን ፡ አገር ፡ ኹሉ ፡ ሰደዱ ።

10 ፤ የጦር ፡ ዕቃውንም ፡ በዐስታሮት ፡ መቅደስ ፡ ውስጥ ፡ አኖሩት ፤ ሬሳውንም ፡ በቤትሳን ፡ ቅጥር ፡ ላይ ፡ አንጠለጠሉት ።

11 ፤ ፍልስጥኤማውያንም ፡ በሳኦል ፡ ላይ ፡ ያደረጉትን ፡ የኢያቢስ ፡ ገለዓድ ፡ ሰዎች ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፤

12 ፤ ዠግናዎች ፡ ሰዎች ፡ ኹሉ ፡ ተነሥተው ፡ ሌሊቱን ፡ ኹሉ ፡ ኼዱ ፤ የሳኦልንም ፡ ሬሳ ፡ የልጆቹንም ፡ ሬሳ ፡ ከቤትሳን ፡
ቅጥር ፡ ላይ ፡ አወረዱ ፤ ወደ ፡ ኢያቢስም ፡ መጡ ፤ በዚያም ፡ አቃጠሉት ።

13 ፤ ዐጥንታቸውንም ፡ ወሰዱ ፡ በኢያቢስም ፡ ባለው ፡ በዐጣጡ ፡ ዛፍ ፡ በታች ፡ ቀበሩት ፤ ሰባት ፡ ቀንም ፡ ጾሙ ፨

# መጽሐፈ ፡ ሳሙኤል ፡ ካልዕ ።

(ክለሳ.1.20020507)

______________መጽሐፈ ፡ ሳሙኤል ፡ ካልዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 1 ። ______________

ምዕራፍ ፡ 1 ።

1 ፤ እንዲህም ፡ ኾነ ፥ ሳኦል ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ ዳዊት ፡ ዐማሌቃውያንን ፡ ከመግደል ፡ ተመልሶ ፡ በጺቅላግ ፡ ኹለት ፡ ቀን ፡ ያኽል ፡ ተቀመጠ ።

2 ፤ በሦስተኛውም ፡ ቀን ፥ እንሆ ፥ ከሳኦል ፡ ሰፈር ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ልብሱን ፡ ቀዶ ፡ በራሱም ፡ ላይ ፡ ትቢያ ፡ ነስንሶ ፡ መጣ ፤ ወደ ፡ ዳዊትም ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ በግንባሩ ፡ ተደፍቶ ፡ እጅ ፡ ነሣ ።

3 ፤ ዳዊትም ፦ ከወዴት ፡ መጣኽ ፧ አለው ፡ ርሱም ፦ ከእስራኤል ፡ ሰፈር ፡ ኰብልዬ ፡ መጣኹ ፡ አለው ።

4 ፤ ዳዊትም ፦ ነገሩ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ኾነ ፧ እስኪ ፡ ንገረኝ ፡ አለው ። ርሱም ፡ መልሶ ፦ ሕዝቡ ፡ ከሰልፉ ፡ ሸሽቷል ፥ ከሕዝቡ ፡ ብዙው ፡ ወደቁ ፡ ሞቱም ፤ ሳኦልና ፡ ልጁም ፡ ዮናታን ፡ ደግሞ ፡ ሞተዋል ፡ አለ ።

5 ፤ ዳዊትም ፡ ወሬኛውን ፡ ጕልማሳ ፦ ሳኦልና ፡ ልጁ ፡ ዮናታን ፡ እንደ ፡ ሞቱ ፡ በምን ፡ ታውቃለኽ ፧ አለው ።

6 ፤ ወሬኛውም ፡ ጕልማሳ ፡ አለ ፦ በድንገት ፡ ወደጊልቦዓ ፡ ተራራ ፡ መጣኹ ፥ እንሆም ፥ ሳኦል ፡ ጦሩን ፡ ተመርኵዞ ፡ ቆሞ ፡ ነበር ፤ ሠረገላዎችና ፡ ፈረሰኛዎችም ፡ ተከትለው ፡ ደረሱበት ።

7 ፤ ወደ ፡ ኋላውም ፡ ዘወር ፡ አለና ፡ እኔን ፡ አይቶ ፡ ጠራኝ ፤ እኔም ፦ እንሆኝ ፡ አልኹ ።

8 ፤ ርሱም ፦ አንተ ፡ ማን ፡ ነኽ ፧ አለኝ ፤ እኔም ፦ ዐማሌቃዊ ፡ ነኝ ፡ ብዬ ፡ መለስኹለት ።

9 ፤ ርሱም ፦ ሰውነቴ ፡ ዝሏልና ፥ ደግሞ ፡ እስከ ፡ አኹን ፡ ድረስ ፡ ነፍሴ ፡ ገና ፡ ፈጽማ ፡ ሕያው ፡ ናትና ፥ በላዬ ፡ ቆመኽ ፡ ግደለኝ ፡ አለኝ ።

10 ፤ እኔም ፡ ከወደቀ ፡ በኋላ ፡ አለ ፡ መዳኑን ፡ አይቼ ፡ በላዩ ፡ ቆሜ ፡ ገደልኹት ፤ በራሱም ፡ ላይ ፡ የነበረውን ፡ ዘውድ ፡ በክንዱም ፡ የነበረውን ፡ ቢተዋ ፡ ወሰድኹ ፥ ወደዚህም ፡ ወደ ፡ ጌታዬ ፡ አመጣኹት ።

11 ፤ ዳዊትና ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ የነበሩ ፡ ሰዎች ፡ ኹሉ ፡ ልብሳቸውን ፡ ይዘው ፡ ቀደዱ ።

12 ፤ በሰይፍም ፡ ወድቀዋልና ፥ ለሳኦልና ፡ ለልጁ ፡ ለዮናታን ፡ ለእግዚአብሔርም ፡ ሕዝብ ፡ ለእስራኤልም ፡ ወገን ፡ እንባ ፡ እያፈሰሱ ፡ አለቀሱ ፥ እስከ ፡ ማታም ፡ ድረስ ፡ ጾሙ ።

13 ፤ ዳዊትም ፡ ወሬኛውን ፡ ጕልማሳ ። አንተ ፡ ከወዴት ፡ ነኽ ፧ አለው ፤ ርሱም ፦ እኔ ፡ የመጻተኛው ፡ የዐማሌቃዊው ፡ ልጅ ፡ ነኝ ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ።

14 ፤ ዳዊትም ፦ እግዚአብሔር ፡ የቀባውን ፡ ለመግደል ፡ እጅኽን ፡ ስትዘረጋ ፡ ለምን ፡ አልፈራኽም ፧ አለው ።

15 ፤ ዳዊትም ፡ ከጕልማሳዎቹ ፡ አንዱን ፡ ጠርቶ ፦ ወደ ፡ ርሱ ፡ ቅረብና ፡ ውደቅበት ፡ አለው ። ርሱም ፡ መታው ፥ ሞተም ።

16 ፤ ዳዊትም ፦ እግዚአብሔር ፡ የቀባውን ፡ እኔ ፡ ገድያለኹ ፡ ብሎ ፡ አፍኽ ፡ በላይኽ ፡ መስክሯልና ፥ ደምኽ ፡ በራስኽ ፡ ላይ ፡ ይኹን ፡ አለው ።

17 ፤ ዳዊትም ፡ ስለ ፡ ሳኦልና ፡ ስለ ፡ ልጁ ፡ ስለ ፡ ዮናታን ፡ ይህን ፡ የሐዘን ፡ ቅኔ ፡ ተቀኘ ፥

18 ፤ የይሁዳንም ፡ ልጆች ፡ ያስተምሩ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ። እንሆ ፥ ይህ ፡ በያሻር ፡ መጽሐፍ ፡ ተጽፏል ።

19 ፤ የእስራኤል ፡ ክብር ፡ በኰረብታዎች ፡ ላይ ፡ ተወግቶ ፡ ሞተ ፤ ኀያላን ፡ እንዴት ፡ ወደቁ!

20 ፤ የፍልስጥኤማውያን ፡ ቈነጃጅርት ፡ ደስ ፡ እንዳይላቸው ፥ የቈላፋንም ፡ ቈነጃጅርት ፡ እልል ፡ እንዳይሉ ፥ በጌት ፡

ውስጥ ፡ አታውሩ ፤ በአስቀሎናም ፡ አደባባይ ፡ የምሥራች ፡ አትበሉ ።

21 ፤ እናንተ ፡ የጊልቦዓ ፡ ተራራዎች ፡ ሆይ ፥ የሳኦል ፡ ጋሻ ፡ በዘይት ፡ እንዳልተቀባ ፥ የኀያላን ፡ ጋሻ ፡ በዚያ ፡
ወድቋልና ፥ ዝናብና ፡ ጠል ፡ አይውረድባችኹ ፥ ቍርባንንም ፡ የሚያበቅል ፡ ዕርሻ ፡ አይኹንባችኹ ።

22 ፤ ከሞቱት ፡ ደምና ፡ ከኀያላን ፡ ስብ ፡ የዮናታን ፡ ቀስት ፡ አልተመለሰችም ፥ የሳኦልም ፡ ሰይፍ ፡ በከንቱ ፡
አልተመለሰም ።

23 ፤ ሳኦልና ፡ ዮናታን ፡ የተዋደዱና ፡ የተስማሙ ፡ ነበሩ ፤ በሕይወታቸውና ፡ በሞታቸው ፡ አልተለያዩም ፤ ከንስር ፡ ይልቅ ፡
ፈጣኖች ፡ ነበሩ ፤ ከአንበሳም ፡ ይልቅ ፡ ብርቱዎች ፡ ነበሩ ።

24 ፤ የእስራኤል ፡ ቈነጃጅት ፡ ሆይ ፥ ቀይ ፡ ሐርና ፡ ጥሩ ፡ ግምጃ ፡ ያለብሳችኹ ፡ ለነበረ ፥ በወርቀ ፡ ዘቦም ፡
ላስጌጣችኹ ፡ ለሳኦል ፡ አልቅሱለት ።

25 ፤ ኀያላንም ፡ በሰልፍ ፡ ውስጥ ፡ እንዴት ፡ ወደቁ! ዮናታንም ፡ በኰረብታዎችኽ ፡ ላይ ፡ ወድቋል ።

26 ፤ ወንድሜ ፡ ዮናታን ፡ ሆይ ፥ እኔ ፡ ስለ ፡ አንተ ፡ እጨነቃለኹ ፤ በእኔ ፡ ዘንድ ፡ ውድኽ ፡ እጅግ ፡ የተለየ ፡
ነበረ ፤ ከሴት ፡ ፍቅር ፡ ይልቅ ፡ ፍቅርኽ ፡ ለእኔ ፡ ግሩም ፡ ነበረ ።

27 ፤ ኀያላን ፡ እንዴት ፡ ወደቁ! የሰልፍም ፡ ዕቃ ፡ እንዴት ፡ ጠፋ!

## መጽሐፈ ፡ ሳሙኤል ፡ ካልዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 2 ።

ምዕራፍ ፡ 2 ።

1 ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ዳዊት ፦ ከይሁዳ ፡ ከተማዎች ፡ ወደ ፡ አንዲቱ ፡ ልውጣን ፡ ብሎ ፡ እግዚአብሔርን ፡
ጠየቀ ። እግዚአብሔርም ፦ ውጣ ፡ አለው ። ዳዊትም ፦ ወዴት ፡ ልውጣ ፡ አለ ። ርሱም ፦ ወደ ፡ ኬብሮን ፡ ውጣ ፡
አለው ።

2 ፤ ዳዊትም ፡ ከኹለቱ ፡ ሚስቶቹ ፡ ከኢይዝራኤላዊቱ ፡ ከአኪናሆምና ፡ የቀርሜሎሳዊው ፡ የናባል ፡ ሚስት ፡ ከነበረችው ፡
ከአቢግያ ፡ ጋራ ፡ ወደዚያ ፡ ወጣ ።

3 ፤ ዳዊትም ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ የነበሩትን ፡ ሰዎችና ፡ ቤት ፡ ሰባቸውን ፡ ዅሉ ፡ አመጣ ፤ በኬብሮንም ፡ ከተማዎች ፡
ተቀመጡ ።

4 ፤ የይሁዳም ፡ ሰዎች ፡ መጥተው ፡ በይሁዳ ፡ ቤት ፡ ይነግሥ ፡ ዘንድ ፡ ዳዊትን ፡ በዚያ ፡ ቀቡት ። ሳኦልን ፡ የቀበሩት ፡
የኢያቢስ ፡ ገለዓድ ፡ ሰዎች ፡ ናቸው ፡ ብለው ፡ ለዳዊት ፡ ነገሩት ።

5 ፤ ዳዊትም ፡ ወደኢያቢስ ፡ ገለዓድ ፡ ሰዎች ፡ መልእክተኛዎችን ፡ ልኮ ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ። እናንተ ፡ ለጌታችኹ ፡
ለሳኦል ፡ ይህን ፡ ቸርነት ፡ አድርጋችኋልና ፥ ቀብራችኹትማልና ፥ በእግዚአብሔር ፡ የተባረካችኹ ፡ ኹኑ ።

6 ፤ አኹንም ፡ እግዚአብሔር ፡ ቸርነትንና ፡ እውነትን ፡ ያድርግላችኹ ፤ ይህንም ፡ ነገር ፡ አድርጋችኋልና ፥ እኔ ፡ ደግሞ ፡
ይህን ፡ ቸርነት ፡ እመልስላችኋለኹ ።

7 ፤ አኹንም ፡ ጌታችኹ ፡ ሳኦል ፡ ሞቷልና ፥ እጃችኹ ፡ ትጽና ፥ እናንተም ፡ ጨክኑ ፤ ዳግም ፡ የይሁዳ ፡ ቤት ፡ በእነርሱ ፡
ላይ ፡ ንጉሥ ፡ እኾን ፡ ዘንድ ፡ ቀብተውኛል ።

8 ፤ የሳኦልም ፡ ጭፍራ ፡ አለቃ ፣ የኔር ፡ ልጅ ፡ አበኔር ፥ የሳኦልን ፡ ልጅ ፣ ኢያቡስቴን ፡ ወስዶ ፡ ወደ ፡ መሃናይም ፡
አሻገረው ፤

9 ፤ በገለዓድና ፡ በአሹራውያን ፡ በኢይዝራኤልም ፡ በኤፍሬምም ፡ በብንያምም ፡ በእስራኤልም ፡ ዅሉ ፡ ላይ ፡ አነገሠው ።

10 ፤ የሳኦል ፡ ልጅ ፡ ኢያቡስቴም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የአርባ ፡ ዓመት ፡ ሰው ፡
ነበረ ፤ ኹለት ፡ ዓመትም ፡ ነገሠ ፤ ነገር ፡ ግን ፥ የይሁዳ ፡ ቤት ፡ ዳዊትን ፡ ተከተለ ።

11 ፤ ዳዊትም ፡ በይሁዳ ፡ ቤት ፡ ነግሦ ፡ በኬብሮን ፡ የተቀመጠበት ፡ ዘመን ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡ ከስድስት ፡ ወር ፡ ነበረ ።

12 ፤ የኔር ፡ ልጅ ፡ አበኔርና ፡ የሳኦል ፡ ልጅ ፡ የኢያቡስቴ ፡ ባሪያዎች ፡ ከመሃናይም ፡ ወደ ፡ ገባዖን ፡ ወጡ ።

13 ፤ የጽሩያ ፡ ልጅ ፡ ኢዮአብና ፡ የዳዊት ፡ ባሪያዎች ፡ ወጥተው ፡ በገባዖን ፡ ውሃ ፡ መቆሚያ ፡ አጠገብ ፡
ተገናኟቸው ፤ በውሃውም ፡ መቆሚያ ፡ በአንዱ ፡ ወገን ፡ እነዚህ ፥ በሌላውም ፡ ወገን ፡ እነዚያ ፡ ኾነው ፡ ተቀመጡ ።

14 ፤ አበኔርም ፡ ኢዮአብን ፦ ጕልማሳዎች ፡ ይነሡ ፥ በፊታችንም ፡ ይቈራቈሱ ፡ አለው ፤ ኢዮአብም ፦ ይነሡ ፡ አለ ።

15 ፤ ለብንያም ፡ ወገንና ፡ ለሳኦል ፡ ልጅ ፡ ለኢያቡስቴ ፡ አስራ ፡ ኹለት ፥ ከዳዊትም ፡ ባሪያዎች ፡ ዐሥራ ፡ ኹለት ፡
ተቈጥረው ፡ ተነሡ ።

16 ፤ ኹሉም ፡ እያንዳንዱ ፡ የወደረኛውን ፡ ራስ ፡ ያዘ ፥ ሰይፉንም ፡ በወደረኛው ፡ ጐን ፡ ሻጠ ፥ ተያይዘውም ፡
ወደቁ ። የዚያም ፡ ስፍራ ፡ ስም ፡ የስለታም ፡ ሰይፍ ፡ ዕርሻ ፡ ተብሎ ፡ ተጠራ ፥ ርሱም ፡ በገባዖን ፡ ነው ።

17 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ ጽኑ ፡ ሰልፍ ፡ ኾነ ፤ በዳዊትም ፡ ባሪያዎች ፡ ፊት ፡ አበኔርና ፡ የእስራኤል ፡ ሰዎች ፡ ተሸነፉ ።

18 ፤ በዚያም ፡ ሦስቱ ፡ የጽሩያ ፡ ልጆች ፡ ኢዮአብና ፡ አቢሳ ፡ ዐሳሄልም ፡ ነበሩ ፤ ዐሳሄልም ፡ እንደ ፡ ዱር ፡ ሚዳቋ ፡
በሩጫ ፡ ፈጣን ፡ ነበረ ።

19 ፤ ዐሳሄልም ፡ የአበኔርን ፡ ፍለጋ ፡ ተከታተለ ፥ አበኔርንም ፡ ከማሳደድ ፡ ቀኝና ፡ ግራ ፡ አላለም ።

20 ፤ አበኔርም ፡ ዘወር ፡ ብሎ ፡ ተመለከተና ፦ አንተ ፡ ዐሳሄል ፡ ነኽን ፧ አለ ። ርሱም ፦ እኔ ፡ ነኝ ፡ አለ ።

21 ፤ አበኔርም ፦ ወደ ፡ ቀኝ ፡ ወይም ፡ ወደ ፡ ግራ ፡ ፈቀቅ ፡ በል ፤ አንድ ፡ ጕልማሳ ፡ ያዝ ፥ መሣሪያውንም ፡ ውሰድ ፡
አለው ። ዐሳሄል ፡ ግን ፡ ርሱን ፡ ከማሳደድ ፡ ፈቀቅ ፡ ይል ፡ ዘንድ ፡ እንቢ ፡ አለ ።

22 ፤ አበኔርም ፡ ዐሳሄልን ፦ ከምድር ፡ ጋራ ፡ እንዳላጣብቅኽ ፡ እኔን ፡ ከማሳደድ ፡ ፈቀቅ ፡ በል ፤ ወደ ፡ ወንድምኽ ፡
ወደ ፡ ኢዮአብ ፡ ፊቴን ፡ አቅኝቼ ፡ አይ ፡ ዘንድ ፡ እንዴት ፡ ይቻለኛል ፧ አለው ።

23 ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ከርሱ ፡ ፈቀቅ ፡ ይል ፡ ዘንድ ፡ እንቢ ፡ አለ ፤ አበኔርም ፡ በጦሩ ፡ ጫፍ ፡ ሆዱን ፡ ወጋው ፥ ጦሩም ፡
በኋላው ፡ ወጣ ፥ በዚያም ፡ ስፍራ ፡ ወድቆ ፡ ሞተ ። ዐሳሄልም ፡ ወድቆ ፡ በሞተበት ፡ ስፍራ ፡ የሚያልፍ ፡ ኹሉ ፡ ይቆም ፡
ነበር ።

24 ፤ ኢዮአብና ፡ አቢሳም ፡ አበኔርን ፡ አሳደዱ ፤ በገባዖንም ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ መንገድ ፡ በጋይ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ እስካለው ፡
እስከ ፡ አማ ፡ ኰረብታ ፡ ድረስ ፡ በወጡ ፡ ጊዜ ፡ ፀሓይ ፡ ጠለቀች ።

25 ፤ የብንያምም ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ አበኔር ፡ ተሰበሰቡ ፥ በአንድነትም ፡ ኾኑ ፥ በኰረብታም ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ቆሙ ።

26 ፤ አበኔርም ፡ ወደ ፡ ኢዮአብ ፡ ጮኾ ፦ ሰይፍ ፡ በእውኑ ፡ እስከ ፡ ዘለዓለም ፡ ያጠፋልን ፧ ፍጻሜውሳ ፡ መራራ ፡ እንደ ፡
ኾነ ፡ አታውቅምን ፧ ሕዝቡ ፡ ወንድሞቻቸውን ፡ ከማሳደድ ፡ ይመለሱ ፡ ዘንድ ፡ ሕዝቡን ፡ የማትናገር ፡ እስከ ፡ መቼ ፡
ነው ፧ አለው ።

27 ፤ ኢዮአብም ፦ ሕያው ፡ እግዚአብሔርን! ባትናገር ፡ ኖሮ ፡ ሕዝቡ ፡ በጧት ፡ ወጥተው ፡ በኼዱ ፡
ነበር ፥ ወንድሞቻቸውንም ፡ ማሳደድ ፡ በተዉ ፡ ነበር ፡ አለ ።

28 ፤ ኢዮአብም ፡ ቀንደ ፡ መለከት ፡ ነፋ ፥ ሕዝቡም ፡ ኹሉ ፡ ቆመ ፥ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ እስራኤልን ፡
አላሳደደም ፥ ሰልፍም ፡ አላደረገም ።

29 ፤ አበኔርና ፡ ሰዎቹም ፡ ሌሊቱን ፡ ኹሉ ፡ ዐረባ ፡ እያለፉ ፡ ኼዱ ፤ ዮርዳኖስንም ፡ ተሻገሩ ፥ ቢትሮንንም ፡ ኹሉ ፡ ካለፉ ፡
በኋላ ፡ ወደ ፡ መሃናይም ፡ መጡ ።

30 ፤ ኢዮአብም ፡ አበኔርን ፡ ከማሳደድ ፡ ተመለሰ ፤ ሕዝቡንም ፡ ኹሉ ፡ ሰበሰበ ፥ ከዳዊትም ፡ ባሪያዎች ፡ ከዐሳሄል ፡ ሌላ ፡
ዐሥራ ፡ ዘጠኝ ፡ ሰዎች ፡ ጐደሉ ።

31 ፤ የዳዊትም ፡ ባሪያዎች ፡ ከብንያምና ፡ ከአበኔር ፡ ሰዎች ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ስድሳ ፡ ያኽል ፡ ገደሉ ።

32 ፤ ዐሳሄልንም ፡ አንሥተው ፡ በቤተ ፡ ልሔም ፡ በአባቱ ፡ መቃብር ፡ ቀበሩት ፤ ኢዮአብና ፡ ሰዎቹም ፡ ሌሊቱን ፡ ኹሉ ፡
ኼዱ ፥ በኬብሮንም ፡ አነጉ ።

መጽሐፈ ፡ ሳሙኤል ፡ ካልዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 3 ።

ምዕራፍ ፡ 3 ።

1 ፤ በሳኦል ፡ ቤትና ፡ በዳዊት ፡ ቤት ፡ መካከል ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ ጦርነት ፡ ኾነ ፤ የዳዊት ፡ ቤት ፡ እየበረታ ፥ የሳኦል ፡ ቤት ፡
ግን ፡ እየደከመ ፡ የሚኼድ ፡ ኾነ ።

2 ፤ ለዳዊትም ፡ ወንድ ፡ ልጆች ፡ በኬብሮን ፡ ተወለዱለት ፤ በኵሩም ፡ ከኢይዝራኤላዊቱ ፡ ከአኪናሖም ፡ የተወለደው ፡
አምኖን[145] ፡ ነበረ ።

3 ፤ ኹለተኛውም ፡ የቀርሜሎሳዊው ፡ የናባል ፡ ሚስት ፡ ከነበረች ፡ ከአቢግያ ፡ የተወለደው ፡ ዶሎሕያ[146] ፡
ነበረ ። ሦስተኛውም ፡ ከጌሹር ፡ ንጉሥ ፡ ከተልማይ[147] ፡ ልጅ ፡ ከመዓካ ፡ የተወለደው ፡ አቤሴሎም[148] ፡ ነበረ ።

4 ፤ አራተኛውም ፡ የአጊት ፡ ልጅ ፡ አዶንያስ ፥ ዐምስተኛውም ፡ የአቢጣል ፡ ልጅ ፡ ሰፋጥያስ ፡ ነበረ ።

5 ፤ ስድስተኛውም ፡ የዳዊት ፡ ልጅ ፡ ሚስት ፡ የዔግላ ፡ ልጅ ፡ ይትረኃም ፡ ነበረ ። እነዚህም ፡ ለዳዊት ፡ በኬብሮን ፡
ተወለዱለት ።

6 ፤ በሳኦል ፡ ቤትና ፡ በዳዊት ፡ ቤት ፡ መካከል ፡ ጦርነት ፡ ኾኖ ፡ ሳለ ፡ አበኔር ፡ በሳኦል ፡ ቤት ፡ ይበረታ ፡ ነበር ።

7 ፤ ለሳኦልም ፡ የኢዮሄል ፡ ልጅ ፡ ሪጽፋ ፡ የተባለች ፡ ቁባት ፡ ነበረችው ፤ ኢያቡስቴም ፡ አበኔርን ፦ ወዳባቴ ፡ ቁባት ፡
ለምን ፡ ገባኽ ፧ አለው ።

8 ፤ አበኔርም ፡ በኢያቡስቴ ፡ ቃል ፡ እጅግ ፡ ተቈጥቶ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፦ እኔ ፡ ለአባትኽ ፡ ለሳኦል ፡ ቤት ፡ ለወንድሞቹም ፡
ለዘመዶቹም ፡ ቸርነት ፡ አድርጌያለኹ ፥ አንተንም ፡ ለዳዊት ፡ እጅ ፡ አሳልፌ ፡ አልሰጠኹም ፤ አንተም ፡ ዛሬ ፡ ከዚች ፡
ሴት ፡ ጋራ ፡ ስለሠራኹት ፡ ኀጢአት ፡ ትከሰኛለኽ ፤ በእውኑ ፡ እኔ ፡ የውሻ ፡ ራስ ፡ ነኝን ፧

9 ፤ 10 ፤ መንግሥትን ፡ ከሳኦል ፡ ቤት ፡ ያወጣ ፡ ዘንድ ፡ የዳዊትንም ፡ ዙፋን ፡ በእስራኤልና ፡ በይሁዳ ፡ ከዳን ፡ ዠምሮ ፡
እስከ ፡ ቤርሳቤሕ ፡ ድረስ ፡ ከፍ ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለዳዊት ፡ እንደ ፡ ማለለት ፡ እንዲሁ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡
ባላደርግ ፡ እግዚአብሔር ፡ በአበኔር ፡ ይህን ፡ ያድርግበት ፡ ይህንም ፡ ይጨምርበት ።

11 ፤ ኢያቡስቴም ፡ አበኔርን ፡ ይፈራው ፡ ነበርና ፥ አንዳች ፡ ይመልስለት ፡ ዘንድ ፡ አልቻለም ።

12 ፤ አበኔርም ፡ ለዳዊት ፦ ምድሪቱ ፡ ለማን ፡ ናት ፧ ከእኔ ፡ ጋራ ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አድርግ ፥ እጄም ፡ ከአንተ ፡ ጋራ ፡
ትኾናለች ፥ እስራኤልንም ፡ ዅሉ ፡ ወዳንተ ፡ እመልሰዋለኹ ፡ ብለው ፡ ይነግሩት ፡ ዘንድ ፡ መልእክተኛዎች ፡ ሰደደለት ።

13 ፤ ዳዊትም ፦ ይኹን ፥ ከአንተ ፡ ጋራ ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አደርጋለኹ ፤ ነገር ፡ ግን ፥ አንድ ፡ ነገር ፡ ከአንተ ፡
እሻለኹ ፤ ፊቴን ፡ ለማየት ፡ በመጣኽ ፡ ጊዜ ፥ የሳኦልን ፡ ልጅ ፡ ሜልኮልን ፡ ካላመጣኽልኝ ፡ ፊቴን ፡ አታይም ፡ አለ ።

14 ፤ ዳዊትም ፡ ወደሳኦል ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ኢያቡስቴ ፦ በመቶ ፡ ፍልስጥኤማውያን ፡ ሸለፈት ፡ ያጨዂትን ፡ ሚስቴን ፡
ሜልኮልን ፡ ስጠኝ ፡ ብሎ ፡ መልእክተኛዎችን ፡ ሰደደ ።

15 ፤ ኢያቡስቴም ፡ ልኮ ፡ ከሌሳ ፡ ልጅ ፡ ከባሏ ፡ ከፈልጢኤል ፡ ወሰዳት ።

16 ፤ ባሏም ፡ እያለቀሰ ፡ ከርሷ ፡ ጋራ ፡ ኼደ ፥ እስከ ፡ ብራቂም ፡ ድረስ ፡ ተከተላት ። አበኔርም ፦ ኺድ ፥ ተመለስ ፡
አለው ፤ ርሱም ፡ ተመለሰ ።

17 ፤ አበኔርም ፡ ለእስራኤል ፡ ሽማግሌዎች ፦ አስቀድሞ ፡ ዳዊት ፡ በእናንተ ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ ይኾን ፡ ዘንድ ፡ ፈልጋችኹ ፡
ነበር ።

18 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ስለ ፡ ዳዊት ፦ በባሪያዬ ፡ በዳዊት ፡ እጅ ፡ ሕዝቤን ፡ እስራኤልን ፡ ከፍልስጥኤማውያን ፡ እጅና ፡
ከጠላቶቻቸው ፡ ዅሉ ፡ እጅ ፡ አድናለኹ ፡ ብሎ ፡ ተናግሯልና ፥ እንግዲህ ፡ አኹን ፡ አድርጉ ፡ ብሎ ፡ ነገራቸው ።

19 ፤ አበኔርም ፡ ደግሞ ፡ በብንያም ፡ ወገን ፡ ጕሮ ፡ ተናገረ ፤ አበኔርም ፡ ደግሞ ፡ በእስራኤልና ፡ በብንያም ፡ ቤት ፡ ዅሉ ፡
መልካም ፡ የነበረውን ፡ ለዳዊት ፡ ሊነግረው ፡ ወደ ፡ ኬብሮን ፡ ኼደ ።

145 አማኝ ።
146 ዕብ. ፥ ኪልአብ ፡ (ከለአ ፡ አበ ፥ ከላ ፡ ከለከለ ፡ አባት) ።
147 ዕብ. ፥ ታልማይ ፡ (ተላሚ ፥ ዐራሽ) ።
148 ዕብ. ፥ አቢሻሎም ፡ (አበ ፡ ሰላም ፥ የሰላም ፡ አባት) ።

20 ፤ አበኔርም ፡ ከኻያ ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ወደ ፡ ኬብሮን ፡ መጣ ። ዳዊትም ፡ ለአበኔርና ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡
ለነበሩት ፡ ሰዎች ፡ ግብዣ ፡ አደረገላቸው ።

21 ፤ አበኔርም ፡ ዳዊትን ፦ ተነሥቼ ፡ ልኺድ ፥ ከአንተ ፡ ጋራም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ እንዲያደርጉ ፥ ነፍስኽም ፡ እንደ ፡
ወደደች ፡ ዅሉን ፡ እንድትገዛ ፡ እስራኤልን ፡ ዅሉ ፡ ለጌታዬ ፡ ለንጉሥ ፡ ልሰብስብ ፡ አለው ። ዳዊትም ፡ አበኔርን ፡
አሰናበተው ፥ በደኅናም ፡ ኼደ ።

22 ፤ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ የዳዊት ፡ ባሪያዎችና ፡ ኢዮአብ ፡ ከዘመቻ ፡ ታላቅ ፡ ምርኮ ፡ ይዘው ፡ መጡ ። አበኔር ፡ ግን ፡
ዳዊት ፡ አሰናብቶት ፡ በደኅና ፡ ኼዶ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ በኬብሮን ፡ አልነበረም ።

23 ፤ ኢዮአብና ፡ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ የነበረ ፡ ጭፍራ ፡ ዅሉ ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፦ የኔር ፡ ልጅ ፡ አበኔር ፡ ወደ ፡ ንጉሥ ፡
መጣ ፥ አሰናበተውም ፡ በደኅናውም ፡ ኼደ ፡ ብለው ፡ ሰዎች ፡ ለኢዮአብ ፡ ነገሩት ።

24 ፤ ኢዮአብም ፡ ወደ ፡ ንጉሥ ፡ ገብቶ ፦ ምን ፡ አደረግኽ ፡፡ እንሆ ፥ አበኔር ፡ መጥቶልኽ ፡ ነበር ፤ በደኅና ፡ እንዲኼድ ፡
ስለ ፡ ምን ፡ አሰናበትኸው ፡፡

25 ፤ የኔር ፡ ልጅ ፡ አበኔር ፡ ያታልልኽ ፡ ዘንድ ፥ መውጫኽንና ፡ መግቢያኽንም ፡ ያውቅ ፡ ዘንድ ፥ የምታደርገውንም ፡
ነገር ፡ ዅሉ ፡ ያስተውል ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ መጣ ፡ አታውቅምን ፡፡ አለው ።

26 ፤ ኢዮአብም ፡ ከዳዊት ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ መልእክተኛዎችን ፡ ከአበኔር ፡ በዃላ ፡ ላከ ፥ ከሴይርም ፡ ጕድጓድም ፡
መለሱት ። ዳዊት ፡ ግን ፡ ይህን ፡ አላወቀም ።

27 ፤ አበኔርም ፡ ወደ ፡ ኬብሮን ፡ በተመለሰ ፡ ጊዜ ፡ ኢዮአብ ፡ በበር ፡ ውስጥ ፡ በቈይታ ፡ ይናገረው ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡
አጠገቡ ፡ ወሰደው ፤ በዚያም ፡ ለወንድሙ ፡ ለዐሳሄል ፡ ደም ፡ ተበቅሎ ፡ ሆዱን ፡ መታው ፥ ሞተም ።

28 ፤ በዃላም ፡ ዳዊት ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ እንደ ፡ ተደረገ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፦ ከኔር ፡ ልጅ ፡ ከአበኔር ፡ ደም ፡ በእግዚአብሔር ፡
ዘንድ ፡ ለዘለዓለም ፡ እኔ ፡ ንጹሕ ፡ ነኝ ፥ መንግሥቴም ፡ ንጹሕ ፡ ነው ፤

29 ፤ በኢዮአብ ፡ ራስ ፡ ላይና ፡ በአባቱ ፡ ቤት ፡ ዅሉ ፡ ላይ ፡ ይምጣበት ፤ በኢዮአብም ፡ ቤት ፡ ፈሳሽ ፡ ነገር ፡ ያለበት ፡
ወይም ፡ ለምጻም ፡ ወይም ፡ ዐንካሳ ፡ ወይም ፡ በሰይፍ ፡ የሚወድቅ ፡ ወይም ፡ እንጀራ ፡ የሌለው ፡ ሰው ፡ አይታጣ ፡ አለ ።

30 ፤ ኢዮአብና ፡ ወንድሙ ፡ አቢሳም ፡ በሰልፍ ፡ በገባዖን ፡ ወንድማቸው ፡ ዐሳሄልን ፡ ገድሎ ፡ ነበርና ፥ አበኔርን ፡
ገደሉት ።

31 ፤ ዳዊትም ፡ ኢዮአብንና ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ የነበሩትን ፡ ሕዝብ ፡ ዅሉ ፦ ልብሳችኹን ፡ ቅደዱ ፥ ማቅም ፡
ልበሱ ፥ በአበኔርም ፡ ፊት ፡ አልቅሱ ፡ አላቸው ። ንጉሡም ፡ ዳዊት ፡ ከቃሬዛው ፡ በዃላ ፡ ኼደ ።

32 ፤ አበኔርንም ፡ በኬብሮን ፡ ቀበሩት ፤ ንጉሡም ፡ ድምፁን ፡ ከፍ ፡ አድርጎ ፡ በአበኔር ፡ መቃብር ፡ አጠገብ ፡
አለቀሰ ፤ ሕዝቡም ፡ ዅሉ ፡ አለቀሱ ። ንጉሡም ፡ ለአበኔር ፦

33 ፤ አበኔር ፡ ሰነፍ ፡ እንደሚሞት ፡ ይሞታልን ፡፡

34 ፤ እጆኽ ፡ አልታሰረም ፥ እግርኽም ፡ በሰንሰለት ፡ አልተያዘም ፤ ሰው ፡ በዐመፀኛዎች ፡ ፊት ፡ እንደሚወድቅ ፡ አንተ ፡
እንዲሁ ፡ ወደቅኽ ፡ ብሎ ፡ የልቅሶ ፡ ቅኔ ፡ ተቀኘለት ። ሕዝቡም ፡ ዅሉ ፡ ዋይታ ፡ አብዝተው ፡ አለቀሱ ።

35 ፤ ሕዝቡም ፡ ዅሉ ፡ ገና ፡ ሳይመሽ ፡ ዳዊትን ፡ እንጀራ ፡ ይበላ ፡ ዘንድ ፡ ሊጋብዙት ፡ መጡ ፤ ዳዊት ፡ ግን ፦ ፀሓይ ፡
ሳትጠልቅ ፡ እንጀራ ፡ ወይም ፡ ሌላ ፡ ነገር ፡ ብቀምስ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይህን ፡ ያድርግብኝ ፥ ይህንም ፡ ይጨምርብኝ ፡
ብሎ ፤ ማለ ።

36 ፤ ሕዝቡም ፡ ዅሉ ፡ ይህን ፡ ተመለከቱ ፥ ደስ ፡ አሠኛቸውም ፤ በሕዝቡም ፡ ዅሉ ፡ ፊት ፡ ንጉሥ ፡ ያደረገው ፡ ዅሉ ፡
ደስ ፡ አሠኛቸው ።

37 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ ሕዝቡ ፡ ዅሉ ፡ እስራኤልም ፡ ዅሉ ፡ የኔር ፡ ልጅ ፡ የአበኔር ፡ ሞት ፡ ከንጉሡ ፡ ዘንድ ፡ እንዳልኾነ ፡
ዐወቁ ።

38 ፤ ንጉሡም ፡ ባሪያዎቹን ፦ ዛሬ ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ መኰንንና ፡ ታላቅ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ወደቀ ፡ አታውቁምን ፡፡

39 ፤ እኔም ፡ ዛሬ ፡ ምንም ፡ ለመንገሥ ፡ የተቀባኹ ፡ ብኾን ፡ ደካማ ፡ ነኝ ፤ እነዚህም ፡ ሰዎች ፡ የጽሩያ ፡ ልጆች ፡
በርትተውብኛል ፤ እግዚአብሔር ፡ ክፉት ፡ በሠራ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ክፋቱ ፡ ይመልስበት ፡ አላቸው ።

## መጽሐፈ ፡ ሳሙኤል ፡ ካልዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 4 ።

ምዕራፍ ፡ 4 ።

1 ፤ የሳኦልም ፡ ልጅ ፡ ኢያቡስቴ ፡ አበኔር ፡ በኬብሮን ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ እጁ ፡ ደከመች ፥ እስራኤላውያንም ፡
ኹሉ ፡ ደነገጡ ።

2 ፤ ለሳኦልም ፡ ልጅ ፡ ለኢያቡስቴ ፡ የጭፍራ ፡ አለቃዎች ፡ የኾኑ ፡ ኹለት ፡ ሰዎች ፡ ነበሩት ፤ የአንዱም ፡ ስም ፡
በዓና ፥ የኹለተኛውም ፡ ስም ፡ ሬካብ ፡ ነበረ ፥ ከብንያምም ፡ ልጆች ፡ የብኤሮታዊው ፡ የሬሞን ፡ ልጆች ፡
ነበሩ ፤ ብኤሮትም ፡ ለብንያም ፡ ተቈጥራ ፡ ነበር ።

3 ፤ ብኤሮታውያንም ፡ ወደ ፡ ጌቴም ፡ ሸሽተው ፡ ነበር ፥ እስከ ፡ ዛሬም ፡ ድረስ ፡ በዚያ ፡ ተጠግተው ፡ ነበር ።

4 ፤ ለሳኦልም ፡ ልጅ ፡ ለዮናታን ፡ አንድ ፡ ሽባ ፡ የኾነ ፡ ልጅ ፡ ነበረው ። የሳኦልና ፡ የዮናታን ፡ ወሬ ፡ ከኢይዝራኤል ፡
በመጣ ፡ ጊዜ ፡ የዐምስት ፡ ዓመት ፡ ልጅ ፡ ነበረ ፥ ሞግዚቱም ፡ ዐዝላው ፡ ሸሸች ፤ ፈጥናም ፡ ስትሸሽ ፡ ወድቆ ፡ ሽባ ፡
ኾነ ። ስሙም ፡ ሜምፊቦስቴ ፡ ነበር ።

5 ፤ የብኤሮታዊውም ፡ የሬሞን ፡ ልጆች ፡ ሬካብና ፡ በዓና ፡ ቀኑ ፡ ሲሞቅ ፡ ወደኢያቡስቴ ፡ ቤት ፡ መጡ ፤ ርሱም ፡ በቀትር ፡
ጊዜ ፡ በምንጣፍ ፡ ላይ ፡ ተኝቶ ፡ ነበር ።

6 ፤ በረኛዪቱም ፡ ስንዴ ፡ ታበጥር ፡ ነበር ፥ አንቀላፍታም ፡ ተኝታ ፡ ነበር ፤ ሬካብና ፡ ወንድሙ ፡ በዓናም ፡ በቀስታ ፡ ገቡ ።

7 ፤ ወደ ፡ ቤትም ፡ በገቡ ፡ ጊዜ ፡ ርሱ ፡ በዕልፍኙ ፡ በምንጣፉ ፡ ላይ ፡ ተኝቶ ፡ ሳለ ፡ መቱት ፥ ገደሉትም ፤ ራሱንም ፡
ቈርጠው ፡ ወሰዱት ፥ በዐረባም ፡ መንገድ ፡ ሌሊቱን ፡ ኹሉ ፡ ኼዱ ።

8 ፤ የኢያቡስቴንም ፡ ራስ ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ወደ ፡ ኬብሮን ፡ መጡ ፥ ንጉሡንም ፡– ነፍስኽን ፡ ይሻ ፡ የነበረው ፡
የጠላትኽ ፡ የሳኦል ፡ ልጅ ፡ የኢያቡስቴ ፡ ራስ ፡ እንሆ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ዛሬ ፡ ከሳኦልና ፡ ከዘሩ ፡ ለጌታችን ፡ ለንጉሥ ፡
ተበቀለለት ፡ አሉት ።

9 ፤ ዳዊትም ፡ ለብኤሮታዊው ፡ ለሬሞት ፡ ልጆች ፡ ለሬካብና ፡ ለወንድሙ ፡ ለበዓና ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
መለሰላቸው ። ነፍሴን ፡ ከመከራ ፡ ኹሉ ፡ ያዳነ ፡ ሕያው ፡ እግዚአብሔርን!

10 ፤ መልካም ፡ ወሬ ፡ የያዘ ፡ መስሎት ፡– እንሆ ፥ ሳኦል ፡ ሞተ ፡ ብሎ ፡ የነገረኝን ፡ የምሥራቹ ፡ ዋጋ ፡ እንዲኾን ፡
ይዤ ፡ በጺቅላግ ፡ ገደልኹት ።

11 ፤ ይልቁንስ ፡ በቤቱ ፡ ውስጥ ፡ በምንጣፉ ፡ ላይ ፡ ንጹሑን ፡ ሰው ፡ የገደላችኹትን ፡ እናንተን ፡ ኀጢአተኛዎችንማ ፡
እንዴት ፡ ነዋ ፤ ደሙን ፡ ከእጃችኹ ፡ አልሻውምን ፤ ከምድርም ፡ አላጠፋችኹምን ፤

12 ፤ ዳዊትም ፡ ጕልማሳዎቹን ፡ አዘዘ ፥ ገደሏቸውም ፤ እጃቸውንና ፡ እግራቸውን ፡ ቈርጠው ፡ በኬብሮን ፡ በውሃ ፡
መቆሚያ ፡ አጠገብ ፡ አንጠለጠሏቸው ። የኢያቡስቴንም ፡ ራስ ፡ ወስደው ፡ በአበኔር ፡ መቃብር ፡ በኬብሮን ፡ ቀበሩት ።

## መጽሐፈ ፡ ሳሙኤል ፡ ካልዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 5 ።

ምዕራፍ ፡ 5 ።

1 ፤ የእስራኤልም ፡ ነገድ ፡ ኹሉ ፡ ወደ ፡ ኬብሮን ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ መጥተው ፡– እንሆ ፥ እኛ ፡ የዐጥንትኽ ፡ ፍላጭ ፡
የሥጋኽ ፡ ቍራጭ ፡ ነን ።

2 ፤ አስቀድሞ ፡ ሳኦል ፡ በእኛ ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ ኾኖ ፡ ሳለ ፡ እስራኤልን ፡ የምታወጣና ፡ የምታገባ ፡ አንተ ፡
ነበርኽ ፤ እግዚአብሔርም ፡– አንተ ፡ ሕዝቤን ፡ እስራኤልን ፡ ትጠብቃለኽ ፥ በእስራኤልም ፡ ላይ ፡ አለቃ ፡ ትኾናለኽ ፡
ብሎኻል ፡ ነበር ፡ አሉት ።

3 ፤ የእስራኤልም ፡ ሽማግሌዎች ፡ ኹሉ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ኬብሮን ፡ መጡ ፤ ንጉሡ ፡ ዳዊትም ፡ በኬብሮን ፡
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ከነርሱ ፡ ጋራ ፡ አደረገ ፤ በእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ይኾን ፡ ዘንድ ፡ ዳዊትን ፡ ቀቡት ።

4 ፤ ዳዊትም ፡ መንገሥ ፡ በዠመረ ፡ ጊዜ ፡ የሠላሳ ፡ ዓመት ፡ ልጅ ፡ ነበረ ፥ አርባ ፡ ዓመትም ፡ ነገሠ ።

5 ፤ በኬብሮን ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡ ከስድስት ፡ ወር ፡ ነገሠ ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ በእስራኤል ፡ ኹሉና ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ ሠላሳ ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ።

6 ፤ ንጉሡና ፡ ሰዎቹም ፡ በአገሩ ፡ ውስጥ ፡ ከተቀመጡት ፡ ከኢያቡሳውያን ፡ ጋራ ፡ ለመዋጋት ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ኼዱ ፤ እነርሱም ፦ ዳዊት ፡ ወደዚህ ፡ ሊገባ ፡ አይችልም ፡ ብለው ፡ ዐስበው ፡ ነበርና ፥ ዳዊትን ፦ ዕውሮችንና ፡ ዐንካሳዎችን ፡ ካላወጣኽ ፡ በቀር ፡ ወደዚህ ፡ አትገባም ፡ አሉት ።

7 ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ዳዊት ፡ ዐምባዪቱን ፡ ጽዮንን ፡ ያዘ ፥ ርሷም ፡ የዳዊት ፡ ከተማ ፡ ናት ።

8 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ ዳዊት ፦ ኢያቡሳውያንን ፡ የሚመታ ፡ በውሃ ፡ መኼጃው ፡ ይውጣ ፤ የዳዊትም ፡ ነፍስ ፡ የምትጠላቸውን ፡ ዕውሮችንና ፡ ዐንካሳዎችን ፡ ያውጣ ፡ አለ ። ስለዚህም ፡ በምሳሌ ፦ ዕውርና ፡ ዐንካሳ ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ አይግቡ ፡ ተባለ ።

9 ፤ ዳዊትም ፡ በዐምባዪቱ ፡ ውስጥ ፡ ተቀመጠ ፥ የዳዊትም ፡ ከተማ ፡ ብሎ ፡ ጠራት ። ዳዊትም ፡ ዙሪያዋን ፡ ከሚሎ ፡ ዠምሮ ፡ ወደ ፡ ውስጥ ፡ ቀጠራት ።

10 ፤ ዳዊትም ፡ እየበረታ ፡ ኼደ ፤ የሰራዊት ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ነበረ ።

11 ፤ የጢሮስም ፡ ንጉሥ ፡ ኪራም ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ መልእክተኛዎችን ፡ የዝግባ ፡ ዕንጨትንም ፡ ዐናጢዎችንም ፡ ጠራቢዎችንም ፡ ላከ ፤ ለዳዊትም ፡ ቤት ፡ ሠሩለት ።

12 ፤ ዳዊትም ፡ እግዚአብሔር ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ አድርጎ ፡ እንዳጸናው ፥ ስለ ፡ ሕዝቡ ፡ ስለ ፡ እስራኤልም ፡ መንግሥቱን ፡ ከፍ ፡ እንዳደረገ ፡ ዐወቀ ።

13 ፤ ዳዊትም ፡ ከኬብሮን ፡ ከመጣ ፡ በኋላ ፡ ሌላዎቹን ፡ ቁባቶቹንና ፡ ሚስቶቹን ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ወሰደ ፤ ለዳዊትም ፡ ደግሞ ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ተወለዱለት ።

14 ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ የተወለዱለት ፡ ስማቸው ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ሳሙስ ፥

15 ፤ ሶባብ ፥ ናታን ፥ ሰሎሞን[149] ፥ ኢያቤሐር ፥ ኤሊሱዔ ፥

16 ፤ ናፌቅ ፥ ያፍያ ፥ ኤሊሳማ ፥ ኤሊዳሄ ፥ ኤሊፋላት ።

17 ፤ ፍልስጥኤማውያንም ፡ ዳዊት ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ ኾኖ ፡ እንደ ፡ ተቀባ ፡ ሰሙ ፥ ፍልስጥኤማውያንም ፡ ኹሉ ፡ ዳዊትን ፡ ሊፈልጉ ፡ ወጡ ፤ ዳዊትም ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ምሽጉ ፡ ወረደ ።

18 ፤ ፍልስጥኤማውያንም ፡ መጥተው ፡ በራፋይም ፡ ሸለቆ ፡ ተበትነው ፡ ሰፈሩ ።

19 ፤ ዳዊትም ፦ ወደ ፡ ፍልስጥኤማውያን ፡ ልውጣን ፡ በእጄስ ፡ አሳልፈኽ ፡ ትሰጣቸዋለኽን ፡ ብሎ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ጠየቀ ። እግዚአብሔርም ፡ ዳዊትን ፦ ፍልስጥኤማውያንን ፡ በርግጥ ፡ በእጅኽ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጣቸዋለኹና ፡ ውጣ ፡ አለው ።

20 ፤ ዳዊትም ፡ ወደ ፡ በዓልፐራሲም ፡ መጣ ፥ በዚያም ፡ መታቸውና ፦ ውሃ ፡ እንዲያፈርስ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጠላቶቼን ፡ በፊቴ ፡ አፈረሳቸው ፡ አለ ። ስለዚህም ፡ የዚያን ፡ ስፍራ ፡ ስም ፡ በዓልፐራሲም ፡ ብሎ ፡ ጠራው ።

21 ፤ ጣዖቶቻቸውንም ፡ በዚያ ፡ ተዉ ፥ ዳዊትና ፡ ሰዎቹም ፡ ወሰዷቸው ።

22 ፤ ፍልስጥኤማውያንም ፡ ደግሞ ፡ መጡ ፥ በራፋይምም ፡ ሸለቆ ፡ ተበትነው ፡ ሰፈሩ ።

23 ፤ ዳዊትም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ጠየቀ ፤ ርሱም ፦ በኋላቸው ፡ ዞረኽ ፡ በሾላው ፡ ዛፍ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ግጠማቸው ፡ እንጂ ፡ አትውጣ ።

24 ፤ በሾላውም ፡ ዛፍ ፡ ራስ ፡ ውስጥ ፡ የሽውሽውታ ፡ ድምፅ ፡ ስትሰማ ፥ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ የፍልስጥኤማውያንን ፡ ጭፍራ ፡ ለመምታት ፡ በፊትኽ ፡ ወጥቶ ፡ ይኾናልና ፥ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ቸኵል ፡ አለው ።

149 ዕብ. ፥ ሽሎሞህ ፡ (ሰላማዊ) ።

25 ፤ ዳዊትም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘው ፡ አደረገ ፤ ከገባዖንም ፡ እስከ ፡ ጌዝር ፡ ድረስ ፡ ፍልስጥኤማውያንን ፡ መታ ።

መጽሐፈ ፡ ሳሙኤል ፡ ካልዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 6 ።

ምዕራፍ ፡ 6 ።

1 ፤ ዳዊትም ፡ ዳግም ፡ ከእስራኤል ፡ የተመረጡትን ፡ ሠላሳ ፡ ሺሕ ፡ ያኽል ፡ ሰው ፡ ሰበሰበ ።

2 ፤ ዳዊትና ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ የነበሩት ፡ ሕዝብ ፡ ኹሉ ፡ በይሁዳ ፡ ካሉ ፡ ከበዓል ፡ ተነሥተው ፡ በኪሩቤል ፡ ላይ ፡ በተቀመጠ ፡ በሰራዊት ፡ ጌታ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ የተጠራውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ታቦት ፡ ከዚያ ፡ ያመጡ ፡ ዘንድ ፡ ኼዱ ።

3 ፤ የእግዚአብሔርንም ፡ ታቦት ፡ በዐዲስ ፡ ሠረገላ ፡ ላይ ፡ ጫኑ ፥ በኰረብታውም ፡ ላይ ፡ ከነበረው ፡ ከዐሚናዳብ ፡ ቤት ፡ አመጡት ፤ የዐሚናዳብ ፡ ልጆችም ፡ ዖዛ ፡ እና ፡ አኂዮ ፡ ዐዲሱን ፡ ሠረገላ ፡ ይነዱ ፡ ነበር ።

4 ፤ በኰረብታውም ፡ ላይ ፡ ከነበረው ፡ ከዐሚናዳብ ፡ ቤት ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ታቦት ፡ ባመጡ ፡ ጊዜ ፡ አኂዮ ፡ በታቦቱ ፡ ፊት ፡ ይኼድ ፡ ነበር ።

5 ፤ ዳዊትና ፡ የእስራኤልም ፡ ቤት ፡ ኹሉ ፡ በቅኔና ፡ በበገና ፡ በመሰንቆም ፡ በከበሮም ፡ በነጋሪትና ፡ በጸናጽል ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በሙሉ ፡ ኀይላቸው ፡ ይጫወቱ ፡ ነበር ።

6 ፤ ወደናኮንም ፡ ዐውድማ ፡ በደረሱ ፡ ጊዜ ፡ በሬዎቹ ፡ ይፋንኑ ፡ ነበርና ፥ ዖዛ ፡ እጁን ፡ ዘርግቶ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ታቦት ፡ ያዘ ።

7 ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቍጣ ፡ በዖዛ ፡ ላይ ፡ ነደደ ፥ እግዚአብሔርም ፡ ስለ ፡ ድፍረቱ ፡ በዚያው ፡ ቀሠፈው ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ታቦት ፡ አጠገብ ፡ በዚያው ፡ ሞተ ።

8 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ዖዛን ፡ ስለ ፡ ሰበረው ፡ ዳዊት ፡ ዐዘነ ፤ እስከ ፡ ዛሬም ፡ ድረስ ፡ የዚያ ፡ ስፍራ ፡ ስም ፡ የዖዛ ፡ ስብራት ፡ ተብሎ ፡ ተጠራ ።

9 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ ዳዊት ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፈራና ፦ የእግዚአብሔር ፡ ታቦት ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዴት ፡ ይመጣል ፡ አለ ።

10 ፤ ዳዊትም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ታቦት ፡ ወደ ፡ ርሱ ፡ ወደዳዊት ፡ ከተማ ፡ ያመጣው ፡ ዘንድ ፡ አልወደደም ፤ ዳዊትም ፡ በጌት ፡ ሰው ፡ በዐቢዳራ[150] ፡ ቤት ፡ አገባው ።

11 ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ታቦት ፡ በጌት ፡ ሰው ፡ በአቢዳራ ፡ ቤት ፡ ሦስት ፡ ወር ፡ ያኽል ፡ ተቀመጠ ፤ እግዚአብሔርም ፡ አቢዳራንና ፡ ቤቱን ፡ ኹሉ ፡ ባረከ ።

12 ፤ ንጉሡ ፡ ዳዊትም ፡ እግዚአብሔር ፡ የአቢዳራን ፡ ቤትና ፡ የነበረውን ፡ ኹሉ ፡ ስለእግዚአብሔር ፡ ታቦት ፡ እንደ ፡ ባረከ ፡ ሰማ ። ዳዊትም ፡ ኼዶ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ታቦት ፡ ከአቢዳራ ፡ ቤት ፡ ወደዳዊት ፡ ከተማ ፡ በደስታ ፡ አመጣው ።

13 ፤ የእግዚአብሔርንም ፡ ታቦት ፡ የተሸከሙ ፡ ስድስት ፡ ርምጃ ፡ በኼዱ ፡ ጊዜ ፡ አንድ ፡ በሬና ፡ አንድ ፡ ፍሪዳ ፡ ሠዋ ።

14 ፤ ዳዊትም ፡ በሙሉ ፡ ኀይሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ይዘፍን ፡ ነበር ፤ ዳዊትም ፡ የበፍታ ፡ ኤፉድ ፡ ለብሶ ፡ ነበር ።

15 ፤ ዳዊትና ፡ የእስራኤልም ፡ ቤት ፡ ኹሉ ፡ ሆ ፡ እያሉ ፡ ቀንደ ፡ መለከትም ፡ እየነፉ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ታቦት ፡ አመጡ ።

16 ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ታቦት ፡ ወደዳዊት ፡ ከተማ ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ የሳኦል ፡ ልጅ ፡ ሜልኮል ፡ በመስኮት ፡ ኾና ፡ ተመለከተች ፥ ንጉሡም ፡ ዳዊት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ሲዘልና ፡ ሲዘፍን ፡ አየች ፤ በልቧም ፡ ናቀችው ።

17 ፤ የእግዚአብሔርንም ፡ ታቦት ፡ አገቡ ፥ ዳዊትም ፡ በተከለለት ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡ በስፍራው ፡ አኖሩት ፤ ዳዊትም ፡ የሚቃጠልና ፡ የደኅንነት ፡ መሥዋዕትን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ አሳረገ ።

18 ፤ ዳዊትም ፡ የሚቃጠልና ፡ የደኅንነት ፡ መሥዋዕት ፡ ማሳረግ ፡ ከፈጸመ ፡ በኋላ ፡ ሕዝቡን ፡ በሰራዊት ፡ ጌታ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ መረቀ ።

150 ዕብ. ፥ ያበድ ፡ ኤዶም ፡ (የኤዶም ፡ አገልጋይ) ።

19 ፤ ለሕዝቡም ፡ ኹሉ ፡ ለእስራኤል ፡ ወገን ፡ ለወንዱም ፡ ለሴቱም ፡ ለያንዳንዱ ፡ አንዳንድ ፡ እንጀራ ፡ አንዳንድም ፡ የሥጋ ፡ ቍራጭ ፡ አንዳንድም ፡ የዘቢብ ፡ ጥፍጥፍ ፡ አከፋፈለ ። ሕዝቡም ፡ ኹሉ ፡ እያንዳንዱ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ኼደ ።

20 ፤ ዳዊትም ፡ ቤተ ፡ ሰቡን ፡ ሊመርቅ ፡ ተመለሰ ። የሳኦልም ፡ ልጅ ፡ ሜልኮል ፡ ዳዊትን ፡ ለመቀበል ፡ ወጣችና ። ምናምንቴዎች ፡ ዕርቃናቸውን ፡ እንደሚገልጡ ፡ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ በባሪያዎቹ ፡ ቈነጃጅት ፡ ፊት ፡ ዕርቃኑን ፡ በመግለጡ ፡ ምንኛ ፡ የተከበረ ፡ ነው! አለችው ።

21 ፤ ዳዊትም ፡ ሜልኮልን ፦ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ዘፍኜለኹ ፤ በእግዚአብሔር ፡ ሕዝብ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ አለቃ ፡ እኾን ፡ ዘንድ ፡ ከአባትሽና ፡ ከቤቱ ፡ ኹሉ ፡ ይልቅ ፡ የመረጠኝ ፡ እግዚአብሔር ፡ የተባረከ ፡ ይኹን ፡ ስለዚህም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እጫወታለኹ ።

22 ፤ አኹንም ፡ ከኾንኹት ፡ ይልቅ ፡ የተናቅኹ ፡ እኾናለኹ ፥ በዐይንሽም ፡ እዋረዳለኹ ፤ ነገር ፡ ግን ፥ በተናገርሽው ፡ ቈነጃጅት ፡ ዘንድ ፡ እከብራለኹ ፡ አላት ።

23 ፤ የሳኦልም ፡ ልጅ ፡ ሜልኮል ፡ እስከሞተችበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ልጅ ፡ አልወለደችም ።

መጽሐፈ ፡ ሳሙኤል ፡ ካልዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 7 ።

ምዕራፍ ፡ 7 ።

1 ፤ እንዲህም ፡ ኾነ ፤ ንጉሡ ፡ በቤቱ ፡ በተቀመጠ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔርም ፡ በዙሪያው ፡ ካሉት ፡ ጠላቶቹ ፡ ኹሉ ፡ ባሳረፈው ፡ ጊዜ ፥

2 ፤ ንጉሡ ፡ ነቢዩን ፡ ናታንን ፦ እኔ ፡ ከዝግባ ፡ በተሠራ ፡ ቤት ፡ ተቀምጫለኹ ፥ የእግዚአብሔር ፡ ታቦት ፡ ግን ፡ በመጋረጃዎች ፡ ውስጥ ፡ እንደ ፡ ተቀመጠ ፡ እይ ፡ አለው ።

3 ፤ ናታንም ፡ ንጉሡን ፦ እግዚአብሔር ፡ ከአንተ ፡ ጋራ ፡ ነውና ፥ ኺድ ፥ በልብኽም ፡ ያለውን ፡ ኹሉ ፡ አድርግ ፡ አለው ።

4 ፤ በዚያም ፡ ሌሊት ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ ናታን ፡ መጣ ፥ እንዲህም ፡ አለው ፦

5 ፤ 6 ፤ ኺድ ፥ ለባሪያዬ ፡ ለዳዊት ፡ ንገረው ፦ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ከግብጽ ፡ ምድር ፡ ካወጣኹበት ፡ ቀን ፡ ዠምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ በድንኳንና ፡ በማደሪያ ፡ እኼድ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ በቤት ፡ አልተቀመጥኹምና ፡ አንተ ፡ የምኖርበትን ፡ ቤት ፡ አትሠራልኝም ።

7 ፤ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ኹሉ ፡ ጋራ ፡ ባለፍኹበት ፡ ስፍራ ፡ ኹሉ ፦ ስለ ፡ ምን ፡ ቤትን ፡ ከዝግባ ፡ ዕንጨት ፡ አልሠራችኹልኝም ፥ ብዬ ፡ ሕዝቤን ፡ እስራኤልን ፡ ይጠብቅ ፡ ዘንድ ፡ ከእስራኤል ፡ ነገድ ፡ ላዘዝኹት ፡ ለአንዱ ፡ በእውኑ ፡ ተናግሬያለኹን ፥

8 ፤ አኹንም ፡ ዳዊትን ፡ ባሪያዬን ፡ እንዲህ ፡ በለው ፦ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ አንተ ፡ መንጋውን ፡ ስትከተል ፡ በሕዝቤ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ አለቃ ፡ ትኾን ፡ ዘንድ ፡ ከበግ ፡ ጥበቃ ፡ ወሰድኹኽ ፤

9 ፤ በኼድኽበትም ፡ ኹሉ ፡ ከአንተ ፡ ጋራ ፡ ነበርኹ ፥ ጠላቶችኽንም ፡ ኹሉ ፡ ከፊትኽ ፡ አጠፋኹ ፤ በምድርም ፡ ላይ ፡ እንዳሉ ፡ እንደ ፡ ታላላቆቹ ፡ ስም ፡ ታላቅ ፡ ስም ፡ አደርግልኻለኹ ።

10 ፤ 11 ፤ ለሕዝቤም ፡ ለእስራኤል ፡ ስፍራ ፡ አደርግለታለኹ ፥ እተክለውማለኹ ፤ በስፍራውም ፡ ይቀመጣል ፥ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ አይናወጥ ፤ እንደ ፡ ቀድሞው ፡ ዘመንና ፡ በሕዝቤ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ፈራጆች ፡ እንዳስነሣኹበት ፡ ጊዜ ፡ ግፈኛዎች ፡ ተመልሰው ፡ አያስጨንቁትም ፤ ከጠላቶችኽም ፡ አሳርፍኻለኹ ። እግዚአብሔርም ፡ ደግሞ ፦ ቤት ፡ እሠራልኻለኹ ፡ ብሎ ፡ ይነግርኻል ።

12 ፤ ዕድሜኽም ፡ በተፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ ከአባቶችኽም ፡ ጋራ ፡ ባንቀላፋኽ ፡ ጊዜ ፥ ከወገብኽ ፡ የሚወጣውን ፡ ዘርኽን ፡ ከአንተ ፡ በኋላ ፡ አስነሣለኹ ፥ መንግሥቱንም ፡ አጸናለኹ ።

13 ፤ ርሱ ፡ ለስሜ ፡ ቤት ፡ ይሠራል ፤ የመንግሥቱንም ፡ ዙፋን ፡ ለዘለዓለም ፡ አጸናለኹ ።

14 ፤ እኔም ፡ አባት ፡ እኾነዋለኹ ፥ ርሱም ፡ ልጅ ፡ ይኾነኛል ፤ ክፉ ፡ ነገርም ፡ ቢያደርግ ፥ ሰው ፡ በሚቀጣበት ፡ በትርና ፡

በሰው ፡ ልጆች ፡ መቀጫ ፡ እገሥጸዋለኹ ፤

15 ፤ ከፊቴም ፡ ከጣልኹት ፡ ከሳኦል ፡ እንዳራቅኹ ፡ ምሕረቴን ፡ ከርሱ ፡ አላርቅም ።

16 ፤ ቤትኽና ፡ መንግሥትኽም ፡ በፊቴ ፡ ለዘለዓለም ፡ ይጠነክራል ፥ ዙፋንኽም ፡ ለዘለዓለም ፡ ይጸናል ።

17 ፤ እንደዚህ ፡ ቃል ፡ ኹሉ ፡ እንደዚህም ፡ ራእይ ፡ ኹሉ ፡ ናታን ፡ ለዳዊት ፡ ነገረው ።

18 ፤ ንጉሡ ፡ ዳዊትም ፡ ገባ ፥ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ተቀምጦ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፦ ጌታዬ ፡ እግዚአብሔር ፡
ሆይ ፥ እስከዚህ ፡ ያደረስኸኝ ፡ እኔ ፡ ማን ፡ ነኝ ፧

19 ፤ ቤቴስ ፡ ምንድር ፡ ነው ፧ ጌታዬ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፥ ይህ ፡ በፊትኽ ፡ ጥቂት ፡ ነበረ ፤ ስለ ፡ ባሪያኽም ፡ ቤት ፡
ደግሞ ፡ ለሩቅ ፡ ዘመን ፡ ተናገርኽ ፤ ጌታዬ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፥ ይህ ፡ የሰው ፡ ሕግ ፡ ነው ።

20 ፤ ጌታዬ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፥ አንተ ፡ ባሪያኽን ፡ ታውቃለኽና ፡ ዳዊትስ ፡ ይናገርኽ ፡ ዘንድ ፡ የሚጨምረው ፡
ምንድር ፡ ነው ፧

21 ፤ ለባሪያኽም ፡ ታስታውቀው ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ቃልኽ ፡ ምክንያትና ፡ እንደ ፡ ልብኽ ፡ ዐሳብ ፡ ይህን ፡ ታላቅ ፡ ነገር ፡
ኹሉ ፡ አደረግኽ ።

22 ፤ ስለዚህም ፥ አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ ሆይ ፥ እንደ ፡ አንተ ፡ ያለ ፡ የለምና ፥ በጆሯችንም ፡ እንደ ፡ ሰማን ፡ ኹሉ ፡ ከአንተ ፡
በቀር ፡ አምላክ ፡ የለምና ፡ አንተ ፡ ታላቅ ፡ ነኽ ።

23 ፤ ለርሱ ፡ ለራሱ ፡ እንዲኾን ፡ ሕዝብን ፡ ይቤዥ ፡ ዘንድ ፡ ለርሱ ፡ ለራሱም ፡ ስም ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፥ በአሕዛብና ፡
በአምላኮቻቸውም ፡ ፊት ፡ ከግብጽ ፡ በተቤዠው ፡ ሕዝብ ፡ ፊት ፡ ተኣምራትንና ፡ ድንቅን ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡
እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ኼደለት ፡ እንደ ፡ ሕዝብኽ ፡ እንደ ፡ እስራኤል ፡ ያለ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ምን ፡ ሕዝብ ፡ አለ ፧

24 ፤ ሕዝብኽንም ፡ እስራኤልን ፡ ለዘለዓለም ፡ ሕዝብ ፡ አድርገኽ ፡ አጽንተኸዋል ፤ አንተም ፥ አቤቱ ፥ አምላክ ፡
ኾነኻቸዋል ።

25 ፤ አቤቱ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፥ አኹንም ፡ ለባሪያኽና ፡ ለቤቱ ፡ የተናገርኸውን ፡ ለዘለዓለም ፡ አጽናው ፥ እንደ ፡
ተናገርኽም ፡ አድርግ ።

26 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ነው ፡ ይባል ፡ ዘንድ ፡ ስምኽ ፡ ለዘለዓለም ፡ ታላቅ ፡
ይኹን ፤ የባሪያኽም ፡ የዳዊት ፡ ቤት ፡ በፊትኽ ፡ የጸና ፡ ይኹን ።

27 ፤ አቤቱ ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ ሆይ ፥ አንተ ፦ እኔ ፡ ቤት ፡ እሠራልኻለኹ ፡ ብለኽ ፡ ለባሪያኽ ፡
ገልጠኻልና ፥ ስለዚህ ፡ ባሪያኽ ፡ ይህችን ፡ ጸሎት ፡ ወዳንተ ፡ ይጸልይ ፡ ዘንድ ፡ በልቡ ፡ ደፈረ ።

28 ፤ ጌታዬ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፥ አኹንም ፡ አንተ ፡ አምላክ ፡ ነኽ ፥ ቃልኽም ፡ እውነት ፡ ነው ፥ ይህንም ፡ መልካም ፡
ነገር ፡ ለባሪያኽ ፡ ተናግረኻል ።

29 ፤ ጌታዬ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፥ አንተ ፡ ተናግረኻልና ፥ አኹን ፡ እንግዲህ ፡ ለዘለዓለም ፡ በፊትኽ ፡ ይኾን ፡ ዘንድ ፡
የባሪያኽን ፡ ቤት ፥ እባክኽ ፥ ባርክ ፤ በበረከትኽም ፡ የባሪያኽ ፡ ቤት ፡ ለዘለዓለም ፡ ይባረክ ።

________________መጽሐፈ ፡ ሳሙኤል ፡ ካልዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 8 ። ________________

ምዕራፍ ፡ 8 ።

1 ፤ ከዚህም ፡ በዃላ ፡ ዳዊት ፡ ፍልስጥኤማውያንን ፡ መታ ፥ አዋረዳቸውም ፤ ከፍልስጥኤማውያንም ፡ እጅ ፡ ሜቴግ ፡
አማ ፡ የተባለችውን ፡ ከተማ ፡ ወሰደ ።

2 ፤ ሞዐብን ፡ መታ ፥ ሞዐባውያንንም ፡ በምድር ፡ ጥሎ ፡ በገመድ ፡ ለፈራቸው ፤ በኹለትም ፡ ገመድ ፡
ለሞት ፥ በአንድም ፡ ገመድ ፡ ሙሉ ፡ ለሕይወት ፡ ለፈራቸው ፤ ሞዐባውያንም ፡ ለዳዊት ፡ ገባሮች ፡ ኾኑ ፥ ግብርም ፡
አመጡለት ።

3 ፤ ዳዊትም ፡ ደግሞ ፡ በኤፍራጥስ ፡ ወንዝ ፡ አጠገብ ፡ የነበረውን ፡ ግዛት ፡ መልሶ ፡ ለመያዝ ፡ በኼደ ፡ ጊዜ ፡ የረአብን ፡
ልጅ ፡ የሱባን ፡ ንጉሥ ፡ አድርዐዛርን ፡ መታ ።

4 ፤ ዳዊትም ፡ ከርሱ ፡ ሺሕ ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ፈረሰኞዎች ፥ ኻያ ፡ ሺሕም ፡ እግረኛዎች ፡ ያዘ ፤ ዳዊትም ፡ የሠረገለኛውን ፡ ፈረስ ፡ ዅሉ ፡ ቋንዣ ፡ ቈረጠ ፤ ለመቶ ፡ ሠረገላ ፡ ብቻ ፡ አስቀረ ።

5 ፤ ከደማስቆም ፡ ሶርያውያን ፡ የሱባን ፡ ንጉሥ ፡ አድርዐዛርን ፡ ሊረዱ ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ ዳዊት ፡ ከሶርያውያን ፡ ኻያ ፡ ኹለት ፡ ሺሕ ፡ ሰዎች ፡ ገደለ ።

6 ፤ ዳዊትም ፡ በደማስቆ ፡ ሶርያ ፡ ጭፍራዎች ፡ አኖረ ፥ ሶርያውያንም ፡ ለዳዊት ፡ ገባሮች ፡ ኾኑ ፥ ግብርም ፡ አመጡለት ፤ እግዚአብሔርም ፡ ዳዊት ፡ በኼደበት ፡ ዅሉ ፡ ድልን ፡ ሰጠው ።

7 ፤ ዳዊትም ፡ ለአድርዐዛር ፡ ባሪያዎች ፡ የነበሩትን ፡ የወርቅ ፡ ጋሻዎች ፡ ወሰደ ፥ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ ይዟቸው ፡ መጣ ።

8 ፤ ንጉሡም ፡ ዳዊት ፡ ከአድርዐዛር ፡ ከተማዎች ፡ ከቤጣሕና ፡ ከቤሮታይ ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ናስ ፡ ወሰደ ።

9 ፤ የሐማትም ፡ ንጉሥ ፡ ቶዑ ፡ ዳዊት ፡ የአድርዐዛርን ፡ ጭፍራ ፡ ዅሉ ፡ እንደ ፡ መታ ፡ ሰማ ።

10 ፤ ቶዑም ፡ ከአድርዐዛር ፡ ጋራ ፡ ዅልጊዜ ፡ ይዋጋ ፡ ነበርና ፥ ዳዊት ፡ አድርዐዛርን ፡ ድል ፡ ስለ ፡ መታ ፡ ቶዑ ፡ ልጁን ፡ አዶራምን ፡ ደኅንነቱን ፡ ይጠይቅ ፡ ዘንድ ፥ ይመርቀውም ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ላከው ፤ ርሱም ፡ የብርና ፡ የወርቅ ፡ የናስም ፡ ዕቃ ፡ ይዞ ፡ መጣ ።

11 ፤ 12 ፤ ንጉሥ ፡ ዳዊትም ፡ ካሸነፋቸው ፡ ከአሕዛብ ፡ ዅሉ ፡ ከሶርያ ፡ ከሞዐብም ፡ ከዐሞንም ፡ ልጆች ፡ ከፍልስጥኤማውያንም ፡ ከዐማሌቅም ፡ ከረአብም ፡ ልጅ ፡ ከሱባ ፡ ንጉሥ ፡ ከአድርዐዛር ፡ ምርኮ ፡ ከቀደሰው ፡ ብርና ፡ ወርቅ ፡ ጋራ ፡ እነዚህን ፡ ደግሞ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቀደሰ ።

13 ፤ ዳዊትም ፡ በተመለሰ ፡ ጊዜ ፡ ከኤዶምያስ ፡ ዐሥራ ፡ ስምንት ፡ ሺሕ ፡ ሰዎች ፡ በጨው ፡ ሸለቆ ፡ ውስጥ ፡ በመምታቱ ፡ ስሙ ፡ ተጠራ ።

14 ፤ በኤዶምያስ ፡ ዅሉ ፡ ጭፍራዎች ፡ አኖረ ፥ ኤዶማውያንም ፡ ዅሉ ፡ ለዳዊት ፡ ገባሮች ፡ ኾኑ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ዳዊት ፡ በሚኼድበት ፡ ዅሉ ፡ ድልን ፡ ሰጠው ።

15 ፤ ዳዊትም ፡ በእስራኤል ፡ ዅሉ ፡ ላይ ፡ ነገሠ ፤ ዳዊትም ፡ ለሕዝቡ ፡ ዅሉ ፡ ፍርድን ፡ ጽድቅን ፡ አደረገላቸው ።

16 ፤ የጽሩያ ፡ ልጅ ፡ ኢዮአብም ፡ የሰራዊት ፡ አለቃ ፡ ነበረ ፤ የአኺሉድም ፡ ልጅ ፡ ኢዮሳፍጥ[151] ፡ ታሪክ ፡ ጸሓፊ ፡ ነበረ ፤

17 ፤ የአኪጦብም ፡ ልጅ ፡ ሳዶቅ ፥ የአቢሜሌክም ፡ ልጅ ፡ አብያታር ፡ ካህናት ፡ ነበሩ ፤ ሰራያም ፡ ጸሓፊ ፡ ነበረ ፤

18 ፤ የዮዳዔ ፡ ልጅ ፡ በናያስ ፡ በከሊታውያንና ፡ በፈሊታውያን ፡ ላይ ፡ ነበረ ፤ የዳዊትም ፡ ልጆች ፡ አማካሪዎች ፡ ነበሩ ።

መጽሐፈ ፡ ሳሙኤል ፡ ካልዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 9 ።

ምዕራፍ ፡ 9 ።

1 ፤ ዳዊትም ፦ ስለ ፡ ዮናታን ፡ ቸርነት ፡ አደርግለት ፡ ዘንድ ፡ ከሳኦል ፡ ቤት ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ቀርቷልን ፧ አለ ።

2 ፤ ከሳኦልም ፡ ቤት ፡ ሲባ ፡ የሚባል ፡ አንድ ፡ ባሪያ ፡ ነበረ ፥ ወደ ፡ ዳዊትም ፡ ጠሩት ፤ ንጉሡም ፦ አንተ ፡ ሲባ ፡ ነኽን ፧ አለው ። ርሱም ፦ እኔ ፡ ባሪያኽ ፡ ነኝ ፡ አለ ።

3 ፤ ንጉሡም ፦ የእግዚአብሔርን ፡ ቸርነት ፡ አደርግለት ፡ ዘንድ ፡ ከሳኦል ፡ ቤት ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ አልቀረምን ፧ አለ ። ሲባም ፡ ንጉሡን ፦ እግሩ ፡ ሽባ ፡ የኾነ ፡ አንድ ፡ የዮናታን ፡ ልጅ ፡ አለ ፡ አለው ።

4 ፤ ንጉሡም ፦ ወዴት ፡ ነው ፧ አለው ፤ ሲባም ፡ ንጉሡን ፦ እንሆ ፥ ርሱ ፡ በሎዶባር ፡ በዓሚኤል ፡ ልጅ ፡ በማኪር ፡ ቤት ፡ አለ ፡ አለው ።

5 ፤ ንጉሡም ፡ ዳዊት ፡ ልኮ ፡ ከሎዶባር ፡ ከዓሚኤል ፡ ልጅ ፡ ከማኪር ፡ ቤት ፡ አስመጣው ።

6 ፤ የሳኦልም ፡ ልጅ ፡ የዮናታን ፡ ልጅ ፡ ሜምፊቦስቴ ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ መጣ ፥ በግንባሩም ፡ ወድቆ ፡ እጅ ፡ ነሣ ፤ ዳዊትም ፦ ሜምፊቦስቴ ፡ ሆይ ፥ አለ ፤ ርሱም ፦ እንሆኝ ፡ ባሪያኽ ፡ አለ ።

7 ፤ ዳዊትም ፦ ስለ ፡ አባትኽ ፡ ስለ ፡ ዮናታን ፡ ቸርነት ፡ ፈጽሜ ፡ አደርግልኻለኹና ፡ አትፍራ ፤ የአባትኽንም ፡ የሳኦልን ፡

151 ዕብ. ፥ የሆሻፋጥ ፡ (አምላክ ፡ ፈረደለት) ።

ምድር ፡ ኹሉ ፡ እመልስልኻለኹ ፥ አንተም ፡ ኹልጊዜ ፡ ከገበታዬ ፡ እንጀራ ፡ ትበላለኽ ፡ አለው ።

8 ፤ ርሱም ፦ የሞተ ፡ ውሻ ፡ ወደምመስል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ የተመለከትኽ ፥ እኔ ፡ ባሪያኽ ፡ ምንድር ፡ ነኝ ፧ ብሎ ፡ እጅ ፡ ነሣ ።

9 ፤ ንጉሡም ፡ የሳኦልን ፡ ባሪያ ፤ ሲባን ፡ ጠርቶ ፦ ለሳኦልና ፡ ለቤቱ ፡ ኹሉ ፡ የነበረውን ፡ ኹሉ ፡ ለጌታኽ ፡ ልጅ ፡ ሰጥቻለኹ ።

10 ፤ አንተና ፡ ልጆችኽ ፡ ሎሌዎችኽም ፡ ምድሩን ፡ ዕረሱለት ፤ ለጌታኽም ፡ ልጅ ፡ እንጀራ ፡ ይኾነው ፡ ዘንድ ፡ ፍሬውን ፡ አግባ ፤ የጌታኽ ፡ ልጅ ፡ ሜምፊቦስቴ ፡ ግን ፡ ኹልጊዜ ፡ ከገበታዬ ፡ ይበላል ፡ አለው ። ለሲባም ፡ ዐሥራ ፡ ዐምስት ፡ ልጆችና ፡ ኻያ ፡ ባሪያዎች ፡ ነበሩት ።

11 ፤ ሲባም ፡ ንጉሡን ፦ ጌታዬ ፡ ንጉሡ ፡ ባሪያውን ፡ እንዳዘዘ ፡ እንዲሁ ፡ ባሪያኽ ፡ ያደርጋል ፡ አለው ። ሜምፊቦስቴም ፡ ከንጉሡ ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ አንዱ ፡ ከዳዊት ፡ ገበታ ፡ ይበላ ፡ ነበር ።

12 ፤ ለሜምፊቦስቴም ፡ ሚካ ፡ የተባለ ፡ ታናሽ ፡ ልጅ ፡ ነበረው ። በሲባም ፡ ቤት ፡ ያሉ ፡ ኹሉ ፡ ለሜምፊቦስቴ ፡ ያገለግሉ ፡ ነበር ።

13 ፤ ሜምፊቦስቴም ፡ ከንጉሥ ፡ ገበታ ፡ ኹልጊዜ ፡ እየበላ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ተቀምጦ ፡ ነበር ፤ ኹለት ፡ እግሩም ፡ ሽባ ፡ ነበረ ።

## መጽሐፈ ፡ ሳሙኤል ፡ ካልዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 10 ።

ምዕራፍ ፡ 10 ።

1 ፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ የዐሞን ፡ ልጆች ፡ ንጉሥ ፡ ሞተ ፥ ልጁም ፡ ሐኖን ፡ በፋንታው ፡ ነገሠ ።

2 ፤ ዳዊትም ፦ አባቱ ፡ ወረታ ፡ እንዳደረገልኝ ፡ እኔ ፡ ለናዖስ ፡ ልጅ ፡ ለሐኖን ፡ ቸርነት ፡ አደርጋለኹ ፡ አለ ። ዳዊትም ፡ አባቱ ፡ ስለ ፡ ሞተ ፡ ሊያጽናናው ፡ ባሪያዎቹን ፡ ላከ ፤ የዳዊትም ፡ ባሪያዎች ፡ ወደዐሞን ፡ ልጆች ፡ አገር ፡ መጡ ።

3 ፤ የዐሞንም ፡ ልጆች ፡ አለቃዎች ፡ ጌታቸውን ፡ ሐኖንን ፦ ዳዊት ፡ አባትኽን ፡ አክብሮ ፡ ሊያጽናናኽ ፡ ባሪያዎቹን ፡ ወዳንተ ፡ የላከ ፡ ይመስልኻልን ፧ ዳዊትስ ፡ ከተማዪቱን ፡ ለመመርመርና ፡ ለመሰለል ፡ ለማጥፋትም ፡ ባሪያዎቹን ፡ የላከ ፡ አይደለምን ፧ አሉት ።

4 ፤ ሐኖንም ፡ የዳዊትን ፡ ባሪያዎች ፡ ወስዶ ፡ የጢማቸውን ፡ ገሚስ ፡ ላጨ ፥ ልብሳቸውንም ፡ እስከ ፡ ወገባቸው ፡ ድረስ ፡ ከኹለት ፡ ቀዶ ፡ ሰደዳቸው ።

5 ፤ ዳዊትም ፡ ያን ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፥ ሰዎቹ ፡ እጅግ ፡ ዐፍረው ፡ ነበርና ፥ ተቀባዮች ፡ ላከ ። ንጉሡም ፦ ጢማችኹ ፡ እስኪያድግ ፡ ድረስ ፡ በኢያሪኮ ፡ ተቀመጡ ፥ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ተመለሱ ፡ አላቸው ።

6 ፤ የዐሞን ፡ ልጆች ፡ በዳዊት ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ተጠሉ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፥ የዐሞን ፡ ልጆች ፡ ልከው ፡ ከሶርያውያን ፡ ከቤትሮዖብና ፡ ከሱባ ፡ ኻያ ፡ ሺሕ ፡ እግረኛዎች ፥ ከመዓካ ፡ ንጉሥም ፡ አንድ ፡ ሺሕ ፡ ሰዎች ፥ ከጦብም ፡ ዐሥራ ፡ ኹለት ፡ ሺሕ ፡ ሰዎች ፡ ቀጠሩ ።

7 ፤ ዳዊትም ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ኢዮአብንና ፡ የኀያላኑን ፡ ሰራዊት ፡ ኹሉ ፡ ላከ ።

8 ፤ የዐሞንም ፡ ልጆች ፡ ወጥተው ፡ በበሩ ፡ መግቢያ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ተሰለፉ ፤ የሱባና ፡ የረአብ ፡ ሶርያውያን ፥ የጦብና ፡ የመዓካም ፡ ሰዎች ፡ ለብቻቸው ፡ በሰፊ ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ነበሩ ።

9 ፤ ኢዮአብም ፡ በፊትና ፡ በኋላ ፡ ሰልፍ ፡ እንደ ፡ ከበበው ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ከእስራኤል ፡ ምርጥ ፡ ምርጦቹን ፡ ኹሉ ፡ መረጠ ፥ በሶርያውያንም ፡ ፊት ፡ ለሰልፍ ፡ አኖራቸው ።

10 ፤ የቀረውንም ፡ ሕዝብ ፡ በወንድሙ ፡ በአቢሳ ፡ እጅ ፡ አድርጎ ፡ በዐሞን ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ ለሰልፍ ፡ አኖራቸው ።

11 ፤ ሶርያውያን ፡ ቢበረቱብኝ ፡ ትረዳኛለኽ ፤ የዐሞን ፡ ልጆች ፡ ቢበረቱብኽ ፡ እኔ ፡ መጥቼ ፡ እረዳኻለኹ ።

12 ፤ አይዞኽ ፤ ስለ ፡ ሕዝባችንና ፡ ስለ ፡ አምላካችንም ፡ ከተማዎች ፡ እንበርታ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ደስ ፡ ያሠኘውን ፡ ያድርግ ፡ አለ ።

13 ፤ ኢዮአብና ፡ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ የነበረው ፡ ሕዝብ ፡ ከሶርያውያን ፡ ጋራ ፡ ሊዋጉ ፡ ቀረቡ ፥ እነርሱም ፡ ከፊቱ ፡ ሸሹ ።

14 ፤ የዐሞንም ፡ ልጆች ፡ ሶርያውያን ፡ እንደ ፡ ሸሹ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ እነርሱ ፡ ደግሞ ፡ ከአቢሳ ፡ ፊት ፡ ሸሹ ፥ ወደ ፡ ከተማዪቱም ፡ ገቡ ፤ ኢዮአብም ፡ ከዐሞን ፡ ልጆች ፡ ዘንድ ፡ ተመልሶ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ መጣ ።

15 ፤ ሶርያውያንም ፡ በእስራኤል ፡ ፊት ፡ እንደ ፡ ተሸነፉ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ በአንድነት ፡ ተሰበሰቡ ።

16 ፤ አድርዐዛርም ፡ ልኮ ፡ በወንዝ ፡ ማዶ ፡ የነበሩትን ፡ ሶርያውያን ፥ አመጣ ፤ ወደ ፡ ዔላምም ፡ መጡ ፥ የአድርዐዛርም ፡ ሰራዊት ፡ አለቃ ፡ ሶባክ ፡ በፊታቸው ፡ ነበረ ።

17 ፤ ዳዊትም ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ እስራኤልን ፡ ኹሉ ፡ ሰበሰበ ፥ ዮርዳኖስንም ፡ ተሻግሮ ፡ ወደዔላም ፡ መጣ ፤ ሶርያውያንም ፡ በዳዊት ፡ ፊት ፡ ተሰልፈው ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ተዋጉ ።

18 ፤ ሶርያውያንም ፡ ከእስራኤል ፡ ፊት ፡ ሸሹ ፤ ዳዊትም ፡ ከሶርያውያን ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ሠረገለኛዎች ፡ አርባ ፡ ሺሕም ፡ ፈረሰኛዎች ፡ ገደለ ፤ የሰራዊቱንም ፡ አለቃ ፡ ሶባክን ፡ መታ ፥ ርሱም ፡ በዚያ ፡ ሞተ ።

19 ፤ ለአድርዐዛርም ፡ የሚገብሩ ፡ ነገሥታት ፡ ኹሉ ፡ በእስራኤል ፡ ፊት ፡ እንደ ፡ ተሸነፉ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ ከእስራኤል ፡ ጋራ ፡ ታረቁ ፥ ገበሩላቸውም ፦ ሶርያውያንም ፡ ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ የዐሞንን ፡ ልጆች ፡ ይረዱ ፡ ዘንድ ፡ ፈሩ ።

## መጽሐፈ ፡ ሳሙኤል ፡ ካልዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 11 ።

ምዕራፍ ፡ 11 ።

1 ፤ እንዲህም ፡ ኾነ ፤ በዓመቱ ፡ መለወጫ ፡ ነገሥታት ፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ በሚወጡበት ፡ ጊዜ ፥ ዳዊት ፡ ኢዮአብን ፡ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ ባሪያዎቹን ፡ እስራኤልንም ፡ ኹሉ ፡ ሰደደ ። የዐሞንም ፡ ልጆች ፡ አገር ፡ አጠፉ ፥ ረባትንም ፡ ከበቡ ፤ ዳዊት ፡ ግን ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ቀርቶ ፡ ነበር ።

2 ፤ እንዲህም ፡ ኾነ ፤ ወደ ፡ ማታ ፡ ጊዜ ፡ ዳዊት ፡ ከምንጣፉ ፡ ተነሣ ፥ በንጉሥም ፡ ቤት ፡ በሰገነት ፡ ላይ ፡ ተመላለሰ ፤ በሰገነቱ ፡ ሳለ ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ ስትታጠብ ፡ አየ ፤ ሴቲቱም ፡ መልከ ፡ መልካም ፡ ነበረች ።

3 ፤ ዳዊትም ፡ ልኮ ፡ ስለ ፡ ሴቲቱ ፡ ጠየቀ ፤ አንድ ፡ ሰውም ፦ ይህች ፡ የኤልያብ ፡ ልጅ ፡ የኬጢያዊው ፡ የኦርዮ[152] ፡ ሚስት ፡ ቤርሳቤሕ ፡ አይደለችምን ፧ አለ ።

4 ፤ ዳዊትም ፡ መልእክተኛዎች ፡ ልኮ ፡ አስመጣት ፤ ወደ ፡ ርሱም ፡ ገባች ፥ ከርኵሰቷም ፡ ነጽታ ፡ ነበርና ፥ ከርሷ ፡ ጋራ ፡ ተኛ ፤ ወደ ፡ ቤቷም ፡ ተመለሰች ።

5 ፤ ሴቲቱም ፡ አረገዘች ፥ ወደ ፡ ዳዊትም ፦ አርግዤያለኹ ፡ ብላ ፡ ላከችበት ።

6 ፤ ዳዊትም ፡ ወደ ፡ ኢዮአብ ፦ ኬጢያዊውን ፡ ኦርዮን ፡ ስደድልኝ ፡ ብሎ ፡ ላከ ። ኢዮአብም ፡ ኦርዮን ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ሰደደው ።

7 ፤ ኦርዮም ፡ ወደ ፡ ርሱ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ዳዊት ፡ የኢዮአብንና ፡ የሕዝቡን ፡ ደኅንነት ፥ ሰልፉም ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ ጠየቀው ።

8 ፤ ዳዊትም ፡ ኦርዮን ፦ ወደ ፡ ቤትኽ ፡ ኺድ ፥ እግርኽንም ፡ ታጠብ ፡ አለው ። ኦርዮም ፡ ከንጉሡ ፡ ቤት ፡ ሲወጣ ፡ ማለፊያ ፡ የንጉሥ ፡ መብል ፡ ተከትሎት ፡ ኼደ ።

9 ፤ ኦርዮ ፡ ግን ፡ ከጌታው ፡ ባሪያዎች ፡ ኹሉ ፡ ጋራ ፡ በንጉሥ ፡ ቤት ፡ ደጅ ፡ ተኛ ፥ ወደ ፡ ቤቱም ፡ አልወረደም ።

10 ፤ ኦርዮ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ አልኼደም ፡ ብለው ፡ ለዳዊት ፡ ነገሩት ፤ ዳዊትም ፡ ኦርዮን ፦ አንተ ፡ ከመንገድ ፡ የመጣኽ ፡ አይደለምን ፧ ስለ ፡ ምን ፡ ወደ ፡ ቤትኽ ፡ አልወረድኽም ፧ አለው ።

11 ፤ ኦርዮም ፡ ዳዊትን ፦ ታቦቱና ፡ እስራኤል ፡ ይሁዳም ፡ በጐጆ ፡ ተቀምጠዋል ፤ ጌታዬ ፡ ኢዮአብና ፡ የጌታዬም ፡ ባሪያዎች ፡ በሰፊ ፡ ሜዳ ፡ ሰፍረዋል ፤ እኔ ፡ ልበላና ፡ ልጠጣ ፡ ወይስ ፡ ከሚስቴ ፡ ጋራ ፡ ልተኛ ፡ ወደ ፡ ቤቴ ፡ እኼዳለኹን ፧ በሕይወትኽና ፡ በሕያው ፡ ነፍስኽ ፡ እምላለኹ! ይህን ፡ ነገር ፡ አላደርገውም ፡ አለው ።

---

152 ዕብ. ፥ ኡሪያህ ፡ (የጌታ ፡ ነበልባል) ።

12 ፤ ዳዊትም ፡ ኦርዮን ፦ ዛሬ ፡ ደግሞ ፡ በዚህ ፡ ተቀመጥ ፥ ነገም ፡ አሰናብትኻለኹ ፡ አለው ። ኦርዮም ፡ በዚያ ፡ ቀንና ፡ በነጋው ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ተቀመጠ ።

13 ፤ ዳዊትም ፡ ጠራው ፥ በፊቱም ፡ በላና ፡ ጠጣ ፥ አሰከረውም ፤ ነገር ፡ ግን ፥ በመሸ ፡ ጊዜ ፡ ወጥቶ ፡ ከጌታው ፡ ባሪያዎች ፡ ጋራ ፡ በምንጣፉ ፡ ላይ ፡ ተኛ ፥ ወደ ፡ ቤቱም ፡ አልወረደም ።

14 ፤ በነጋም ፡ ጊዜ ፥ ዳዊት ፡ ለኢዮአብ ፡ ደብዳቤ ፡ ጻፈ ፥ በኦርዮም ፡ እጅ ፡ ላከው ።

15 ፤ በደብዳቤውም ፦ ኦርዮን ፡ ጽኑ ፡ ሰልፍ ፡ ባለበት ፡ በፊተኛው ፡ ስፍራ ፡ አቁሙት ፥ ተመቶም ፡ ይሞት ፡ ዘንድ ፡ ከኋላው ፡ ሽሹ ፡ ብሎ ፡ ጻፈ ።

16 ፤ ኢዮአብም ፡ ከተማዪቱን ፡ በከበበ ፡ ጊዜ ፥ ኀያላን ፡ እንዳሉበት ፡ በሚያውቀው ፡ ስፍራ ፡ ኦርዮን ፡ አቆመው ።

17 ፤ የከተማዪቱም ፡ ሰዎች ፡ ወጥተው ፡ ከኢዮአብ ፡ ጋራ ፡ ተዋጉ ፤ ከዳዊትም ፡ ባሪያዎች ፡ ከሕዝቡ ፡ አንዳንዱ ፡ ወደቀ ፤ ኬጢያዊው ፡ ኦርዮም ፡ ደግሞ ፡ ሞተ ።

18 ፤ ኢዮአብም ፡ ልኮ ፡ በሰልፍ ፡ የኾነውን ፡ ኹሉ ፡ ለዳዊት ፡ ነገረው ።

19 ፤ ለመልእክተኛውም ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ አዘዘው ። የሰልፉን ፡ ነገር ፡ ኹሉ ፡ ለንጉሡ ፡ ነግረኽ ፡ በፈጸምኽ ፡ ጊዜ ፦

20 ፤ ስትዋጉ ፡ ወደ ፡ ከተማዪቱ ፡ ለምን ፡ ቀረባችኹ ፧ ከቅጥሩ ፡ በላይ ፡ ፍላጻ ፡ እንዲወረውር ፡ አታውቁምን ፧

21 ፤ የሩቤሼትን ፡ ልጅ ፡ አቢሜሌክን ፡ ማን ፡ ገደለው ፧ ከቅጥር ፡ ላይ ፡ የወፍጮ ፡ መጅ ፡ ጥላ ፡ በቴቤስ ፡ ላይ ፡ የገደለችው ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ አይደለችምን ፧ ስለ ፡ ምን ፡ ወደ ፡ ቅጥሩ ፡ እንደዚህ ፡ ቀረባችኹ ፧ ብሎ ፡ ንጉሡ ፡ ሲቈጣ ፡ ብታይ ፥ አንተ ፦ ባሪያኽ ፡ ኬጢያዊው ፡ ኦርዮ ፡ ደግሞ ፡ ሞተ ፡ በለው ።

22 ፤ መልእክተኛውም ፡ ተነሥቶ ፡ ኼደ ፥ ኢዮአብም ፡ ያዘዘውን ፡ ኹሉ ፡ ለዳዊት ፡ ነገረው ።

23 ፤ መልእክተኛውም ፡ ዳዊትን ፦ ሰዎቹ ፡ በረቱብን ፥ ወደ ፡ሜዳም ፡ ወጡብን ፤ እኛም ፡ ወደቅንባቸው ፥ እስከከተማዪቱም ፡ በር ፡ ድረስ ፡ ተከተልናቸው ።

24 ፤ ፍላጻ ፡ የሚወረውሩም ፡ በቅጥሩ ፡ ላይ ፡ ኾነው ፡ በባሪያዎችኽ ፡ ላይ ፡ ወረወሩ ፤ ከንጉሡም ፡ ባሪያዎች ፡ አንዳንድ ፡ ሞቱ ፥ ባሪያኽም ፡ ኬጢያዊው ፡ ኦርዮ ፡ ደግሞ ፡ ሞተ ፡ አለው ።

25 ፤ ዳዊትም ፡ መልእክተኛውን ፦ ሰይፍ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ይህን ፡ አንድ ፡ ጊዜም ፡ ያን ፡ ያጠፋልና ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ በዐይንኽ ፡ አይክፋ ፤ ከተማዪቱን ፡ የሚወጉትን ፡ አበርታ ፥ አፍርሳትም ፡ብለኽ ፡ ለኢዮአብ ፡ ንገረው ፤ አንተም ፡ አጽናው ፡ አለው ።

26 ፤ የኦርዮም ፡ሚስት ፡ ባሏ ፡ ኦርዮ ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ በሰማች ፡ ጊዜ ፥ ለባሏ ፡ አለቀሰች ።

27 ፤ የልቅሶዋም ፡ ወራት ፡ ሲፈጸም ፡ ዳዊት ፡ ልኮ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ አስመጣት ፥ ሚስትም ፡ ኾነችው ፥ ወንድ ፡ ልጅም ፡ ወለደችለት ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ዳዊት ፡ ያደረገው ፡ ነገር ፡ ኹሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ ኾነ ።

መጽሐፈ ፡ ሳሙኤል ፡ ካልዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 12 ።

ምዕራፍ ፡ 12 ።

1 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ናታንን ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፡ ላከ ፥ ወደ ፡ ርሱም ፡ መጥቶ ፡ አለው ፦ ባንድ ፡ ከተማ ፡ አንዱ ፡ ባለጠጋ ፡ አንዱም ፡ ድኻ ፡ የኾኑ ፡ ኹለት ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ።

2 ፤ ባለጠጋውም ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ በግና ፡ ላም ፡ ነበረው ።

3 ፤ ለድኻው ፡ ግን ፡ ከገዛት ፡ አንዲት ፡ ታናሽ ፡ በግ ፡ በቀር ፡ አንዳች ፡ አልነበረውም ፤ አሳደጋትም ፥ ከልጆቹም ፡ ጋራ ፡ በርሱ ፡ ዘንድ ፡ አደገች ፤ እንጀራውንም ፡ ትበላ ፥ ከዋንጫውም ፡ ትጠጣ ፥ በብብቱም ፡ ትተኛ ፡ ነበር ፥ እንደ ፡ ልጁም ፡ ነበረች ።

4 ፤ ወደ ፡ ባለጠጋውም ፡ እንግዳ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ከበጉና ፡ ከላሙ ፡ ወስዶ ፡ ለዚያ ፡ ወደ ፡ ርሱ ፡ ለመጣው ፡ እንግዳ ፡ ያዘጋጅለት ፡ ዘንድ ፡ሣሣ ፤ የዚያንም ፡ የድኻውን ፡ ሰው ፡ በግ ፡ ወስዶ ፡ ለዚያ ፡ ለመጣው ፡ ሰው ፡ አዘጋጀ ።

5 ፤ ዳዊትም ፡ በዚያ ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ እጅግ ፡ ተቈጥቶ ፡ ናታንን ፦ ሕያው ፡ እግዚአብሔርን! ይህን ፡ ያደረገ ፡ ሰው ፡
የሞት ፡ ልጅ ፡ ነው ።

6 ፤ ይህን ፡ አድርጓልና ፥ አላዘነምና ፡ ስለ ፡ አንዲቱ ፡ በግ ፡ አራት ፡ ይመልስ ፡ አለው ።

7 ፤ ናታንም ፡ ዳዊትን ፡ አለው ፦ ያ ፡ ሰው ፡ አንተ ፡ ነህ ። የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡
ይላል ፦ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ ልትኾን ፡ ቀባኹኽ ፥ ከሳኦልም ፡ እጅ ፡ አዳንኹኽ ፤

8 ፤ የጌታኽንም ፡ ቤት ፡ ሰጠኹኽ ፥ የጌታኽንም ፡ ሚስቶች ፡ በብብትኽ ፡ ጣልኹልኽ ፤ የእስራኤልንና ፡ የይሁዳን ፡ ቤት ፡
ሰጠኹኽ ፤ ይህም ፡ አንሶ ፡ ቢኾን ፡ ኖሮ ፡ ከዚህ ፡ የበለጠ ፡ እጨምርልኽ ፡ ነበር ።

9 ፤ አኹንስ ፡ በፊቱ ፡ ክፉ ፡ ትሠራ ፡ ዘንድ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ነገር ፡ ለምን ፡ አቃለልኽ ፡፡ ኬጢያዊውን ፡ ኦርዮን ፡
በሰይፍ ፡ መትተኻል ፥ ሚስቱንም ፡ ለአንተ ፡ ሚስት ፡ ትኾን ፡ ዘንድ ፡ ወስደኻል ፤ ርሱንም ፡ በዐሞን ፡ ልጆች ፡ ሰይፍ ፡
ገድለኻል ።

10 ፤ ስለዚህም ፡ አቃለኽኛልና ፥ የኬጢያዊውንም ፡ የኦርዮን ፡ ሚስት ፡ ለአንተ ፡ ሚስት ፡ ትኾን ፡ ዘንድ ፡ ወስደኻልና ፡
ለዘለዓለም ፡ ከቤትኽ ፡ ሰይፍ ፡ አይርቅም ።

11 ፤ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ እንሆ ፥ ከቤትኽ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አስነሣብኻለኹ ፤ ሚስቶችኽንም ፡ በዐይንኽ ፡
ፊት ፡ እወስዳለኹ ፥ ለዘመድኽም ፡ እሰጣቸዋለኹ ፥ በዚችም ፡ ፀሓይ ፡ ዐይን ፡ ፊት ፡ ከሚስቶችኽ ፡ ጋራ ፡ ይተኛል ።

12 ፤ አንተ ፡ ይህን ፡ በስውር ፡ አድርገኸዋል ፤ እኔ ፡ ግን ፡ ይህን ፡ በእስራኤል ፡ ኹሉ ፡ ፊትና ፡ በፀሓይ ፡ ፊት ፡
አደርገዋለኹ ።

13 ፤ ዳዊትም ፡ ናታንን ፦ እግዚአብሔርን ፡ በድያለኹ ፡ አለው ። ናታንም ፡ ዳዊትን ፦ እግዚአብሔር ፡ ደግሞ ፡
ኀጢአትኽን ፡ አርቆልኻል ፤ አትሞትም ።

14 ፤ ነገር ፡ ግን ፥ በዚህ ፡ ነገር ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ጠላቶች ፡ ታላቅ ፡ የስድብ ፡ ምክንያት ፡ አድርገኻልና ፡ ስለዚህ ፡
ደግሞ ፡ የተወለደልኽ ፡ ልጅ ፡ ፈጽሞ ፡ ይሞታል ፡ አለው ።

15 ፤ ናታንም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ተመለሰ ። እግዚአብሔርም ፡ የኦርዮ ፡ ሚስት ፡ ለዳዊት ፡ የወለደችውን ፡ ሕፃን ፡
ቀሠፈ ፥ እጅግም ፡ ታመ ፡ ነበር ።

16 ፤ ዳዊትም ፡ ስለ ፡ ሕፃኑ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለመነ ፤ ዳዊትም ፡ ጾመ ፥ ገብቶም ፡ በመሬት ፡ ላይ ፡ ተኛ ።

17 ፤ የቤቱም ፡ ሽማግሌዎች ፡ ተነሥተው ፡ ከምድር ፡ ያነሡት ፡ ዘንድ ፡ በአጠገቡ ፡ ቆሙ ፤ ርሱ ፡ ግን ፡ እንቢ ፡
አለ ፥ ከነርሱም ፡ ጋራ ፡ እንጀራ ፡ አልበላም ።

18 ፤ በሰባተኛውም ፡ ቀን ፡ ሕፃኑ ፡ ሞተ ። የዳዊትም ፡ ባሪያዎች ። ሕፃኑ ፡ በሕይወት ፡ ሳለ ፡ ብንነግረው ፡
አልሰማንም ፤ ይልቁንስ ፡ ሕፃኑ ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ ብንነግረው ፡ እንዴት ፡ ይኾን ፡፡ በነፍሱ ፡ ክፉ ፡ ያደርጋል ፡ ብለው ፡
ሕፃኑ ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ ይነግሩት ፡ ዘንድ ፡ ፈሩ ።

19 ፤ ዳዊትም ፡ ባሪያዎቹ ፡ በሹክሹክታ ፡ ሲነጋገሩ ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ዳዊት ፡ ሕፃኑ ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ ዐወቀ ፤ ዳዊትም ፡
ባሪያዎቹን ፦ ሕፃኑ ፡ ሞቷል ፡፡ አላቸው ። እነርሱም ፦ ሞቷል ፡ አሉት ።

20 ፤ ዳዊትም ፡ ከምድር ፡ ተነሥቶ ፡ ታጠበ ፥ ተቀባም ፥ ልብሱንም ፡ ለወጠ ፤ ወደእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ ገብቶ ፡
ሰገደ ። ወደ ፡ ቤቱም ፡ መጣ ፦ እንጀራ ፡ አምጡልኝ ፡ አለ ፤ በፊቱም ፡ አቀረቡለት ፥ በላም ።

21 ፤ ባሪያዎቹም ፦ ይህ ፡ ያደረግኸው ፡ ነገር ፡ ምንድር ፡ ነው ፡፡ በሕይወት ፡ ሳለ ፡ ስለ ፡ ሕፃኑ ፡ ጾምኽና ፡
አለቀስኽ ፤ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ተነሥተኽ ፡ እንጀራ ፡ በላኽ ፡ አሉት ።

22 ፤ ርሱም ፦ ሕፃኑ ፡ ሕያው ፡ ሳለ ። እግዚአብሔር ፡ ይምረኝ ፥ ሕፃኑም ፡ በሕይወት ፡ ይኖር ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ ማን ፡
ያውቃል ፡፡ ብዬ ፡ ጾምኹ ፡ አለቀስኹም ።

23 ፤ አኹን ፡ ግን ፡ ሞቷል ፤ የምጾመው ፡ ስለ ፡ ምንድር ፡ ነው ፡፡ በእውኑ ፡ እንግዲህ ፡ እመልሰው ፡ ዘንድ ፡
ይቻለኛልን ፡፡ እኔ ፡ ወደ ፡ ርሱ ፡ እኼዳለኹ ፡ እንጂ ፡ ርሱ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አይመለስም ፡ አለ ።

24 ፤ ዳዊትም ፡ ሚስቱን ፡ ቤርሳቤሕን ፡ አጽናናት ፥ ወደ ፡ ርሷም ፡ ገባ ፥ ከርሷም ፡ ጋራ ፡ ተኛ ፤ ወንድ ፡ ልጅም ፡
ወለደች ፥ ስሙንም ፡ ሰሎሞን ፡ ብሎ ፡ ጠራው ። እግዚአብሔርም ፡ ወደደው ፤

25 ፤ ደግሞም ፡ በነቢዩ ፡ በናታን ፡ እጅ ፡ ልኮ ፡ ስሙን ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይዲድያ ፡ ብሎ ፡ ጠራው ።

26 ፤ ኢዮአብም ፡ የዐሞንን ፡ ልጆች ፡ ከተማ ፡ ረባትን ፡ ወጋ ፥ የውሃውንም ፡ ከተማ ፡ ያዘ ።

27 ፤ ኢዮአብም ፡ ወደ ፡ ዳዊት ፦ ረባትን ፡ ወግቻለኹ ፥ የውሃውንም ፡ ከተማ ፡ ይዣለኹ ።

28 ፤ አኹንም ፡ ከተማዪቱን ፡ እንዳልይዝ ፥ በስሜም ፡ እንዳትጠራ ፥ የቀረውን ፡ ሕዝብ ፡ ሰብስብ ፥ ከተማዪቱንም ፡
ከበኽ ፡ ያዝ ፡ ብሎ ፡ መልእክተኛዎችን ፡ ላከ ።

29 ፤ ዳዊትም ፡ ሕዝቡን ፡ ዅሉ ፡ ሰብስቦ ፡ ወደ ፡ ረባት ፡ ኼደ ፥ ወግቶም ፡ ያዛት ።

30 ፤ የንጉሣቸውንም ፡ ዘውድ ፡ ከራሱ ፡ ላይ ፡ ወሰደ ። ክብደቱም ፡ አንድ ፡ መክሊት ፡ ወርቅ ፡ ያኽል ፡ ነበር ፥ ክቡር ፡
ዕንቍም ፡ ነበረበት ፤ ዳዊትም ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ አደረገው ። ከከተማዪቱም ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ምርኮ ፡ አወጣ ።

31 ፤ በውስጧም ፡ የነበሩትን ፡ ሕዝብ ፡ አውጥቶ ፡ በመጋዝና ፡ በብረት ፡ መቈፈሪያና ፡ በብረት ፡ መጥረቢያ ፡ እንዲሠሩ ፡
አደረጋቸው ፤ የሸክላ ፡ ጡብም ፡ እንዲያቃጥሉ ፡ አደረጋቸው ፤ በዐሞን ፡ ልጆች ፡ ከተማዎች ፡ ዅሉ ፡ እንዲህ ፡
አደረገ ። ዳዊትም ፡ ሕዝቡም ፡ ዅሉ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ተመለሱ ።

## መጽሐፈ ፡ ሳሙኤል ፡ ካልዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 13 ።

ምዕራፍ ፡ 13 ።

1 ፤ ከዚህም ፡ በዃላ ፡ እንዲህ ፡ ኾነ ፤ ለዳዊት ፡ ልጅ ፡ ለአቤሴሎም ፡ አንዲት ፡ የተዋበች ፡ እኅት ፡ ነበረችው ፥ ስሟም ፡
ትዕማር ፡ ነበረ ፤ የዳዊትም ፡ ልጅ ፡ አምኖን ፡ ወደዳት ።

2 ፤ አምኖንም ፡ ከእኅቱ ፡ ከትዕማር ፡ የተነሣ ፡ እጅግ ፡ ስለ ፡ ተከዘ ፡ ታመመ ፤ ድንግልም ፡ ነበረችና ፡ አንዳች ፡
ያደርጋት ፡ ዘንድ ፡ በዐይኑ ፡ ፊት ፡ ጭንቅ ፡ ኾኖበት ፡ ነበር ።

3 ፤ ለአምኖንም ፡ የዳዊት ፡ ወንድም ፡ የሳምዓ ፡ ልጅ ፡ ኢዮናዳብ ፡ የሚባል ፡ ወዳጅ ፡ ነበረው ፤ ኢዮናዳብም ፡ እጅግ ፡
ብልኅ ፡ ሰው ፡ ነበረ ።

4 ፤ ርሱም ፦ የንጉሥ ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ ስለ ፡ ምን ፡ ቀን ፡ በቀን ፡ እንዲህ ፡
ከሳኽ ፧ አትነግረኝምን ፧ አለው ። አምኖንም ፦ የወንድሜን ፡ የአቤሴሎምን ፡ እኅት ፡ ትዕማርን ፡ እወዳታለኹ ፡ አለው ።

5 ፤ ኢዮናዳብም ፦ ታምሜያለኹ ፡ ብለኽ ፡ በዐልጋኽ ፡ ላይ ፡ ተኛ ፤ አባትኽም ፡ ሊያይኽ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፦ እኅቴ ፡
ትዕማር ፡ እንድትመጣና ፡ እኔ ፡ የምበላውን ፡ እንጀራ ፡ እንድትሰጠኝ ፥ መብሉንም ፡ እኔ ፡ እያየኹ ፡
እንድታዘጋጅልኝ ፥ ከእጇም ፡ እንድበላው ፡ እለምንኻለኹ ፡ በል ፡ አለው ።

6 ፤ እንዲሁም ፡ አምኖን ፦ ታምሜያለኹ ፡ ብሎ ፡ ተኛ ፤ ንጉሡም ፡ ሊያየው ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ አምኖን ፡
ንጉሡን ፦ እኅቴ ፡ ትዕማር ፡ እንድትመጣና ፡ እኔ ፡ እያየኹ ፡ ኹለት ፡ ዕንጐቻ ፡ እንድታደርግልኝ ፥ ከእጇም ፡ እንድበላ ፡
እለምንኻለኹ ፡ አለው ።

7 ፤ ዳዊትም ፦ መብልን ፡ ታዘጋጂለት ፡ ዘንድ ፡ ወደወንድምሽ ፡ ወደአምኖን ፡ ቤት ፡ ኺጂ ፡ ብሎ ፡ መልእክተኛዎችን ፡
ወደትዕማር ፡ ቤት ፡ ላከ ።

8 ፤ ትዕማርም ፡ ወደወንድሟ ፡ ወደአምኖን ፡ ቤት ፡ ኼደች ፥ ተኝቶም ፡ ነበር ፤ ዱቄትም ፡ ወስዳ ፡ ለወሰች ፥ እያየም ፡
ዕንጐቻ ፡ አደረገች ፥ ጋገረችም ።

9 ፤ ምጣዱንም ፡ ወስዳ ፡ በፊቱ ፡ ገለበጠች ፡ ርሱ ፡ ግን ፡ ይበላ ፡ ዘንድ ፡ እንቢ ፡ አለ ። አምኖንም ፦ ሰውን ፡ ዅሉ ፡
ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ አስወጡ ፡ አለ ፤ ሰውም ፡ ዅሉ ፡ ከርሱ ፡ ዘንድ ፡ ወጣ ።

10 ፤ አምኖንም ፡ ትዕማርን ፦ ከእጅሽ ፡ እበላ ፡ ዘንድ ፡ መብሉን ፡ ወደ ፡ ዕልፍኙ ፡ አግቢው ፡ አላት ፤ ትዕማርም ፡
የሠራችውን ፡ ዕንጐቻ ፡ ወስዳ ፡ ወንድሟ ፡ አምኖን ፡ ወዳለበት ፡ ዕልፍኝ ፡ አገባችው ።

11 ፤ መብሉንም ፡ ባቀረበች ፡ ጊዜ ፡ ያዛትና ፦ እኅቴ ፡ ሆይ ፥ ነዪ ፥ ከእኔም ፡ ጋራ ፡ ተኚ ፡ አላት ።

12 ፤ ርሷ ፡ መልሳ ፦ ወንድሜ ፡ ሆይ ፥ አይኾንም ፤ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ አይገባምና ፡
አታሳፍረኝ ፤ ይህንም ፡ ነውረኛ ፡ ሥራ ፡ አታድርግ ።

13 ፤ እኔም ፡ ነውሬን ፡ ወዴት ፡ ልሸከም ፧ አንተም ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ከምናምንቴዎች ፡ እንደ ፡ አንዱ ፡
ትኾናለኽ ፤ እንግዲህስ ፡ ለንጉሡ ፡ ንገረው ፥ እኔንም ፡ አይነሣኽም ፡ አለችው ።

14 ፤ ቃሏን ፡ ግን ፡ አልሰማም ፤ ከርሷም ፡ ይልቅ ፡ ብርቱ ፡ ነበረና ፡ በግድ ፡ አስነወራት ፥ ከርሷም ፡ ጋራ ፡ ተኛ ።

15 ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ አምኖን ፡ ፈጽሞ ፡ ጠላት ፤ አስቀድሞም ፡ ከወደዳት ፡ ውድ ፡ ይልቅ ፡ በኋላ ፡ የጠላት ፡ ጥል ፡
በለጠ ። አምኖንም ፦ ተነሥተሽ ፡ ኺጂ ፡ አላት ።

16 ፤ ርሷም ፦ አይኾንም ፤ ቀድሞ ፡ ከሠራኸው ፡ ክፋት ፡ ይልቅ ፡ እኔን ፡ በማውጣትኽ ፡ የበለጠ ፡ ክፋት ፡ ትሠራለኽ ፡
አለችው ፤ ርሱ ፡ ግን ፡ አልሰማትም ።

17 ፤ የሚያገለግለውንም ፡ ብላቴና ፡ ጠርቶ ፦ ይህችን ፡ ሴት ፡ ከፊቴ ፡ አስወጥተኽ ፡ በሩን ፡ ዝጋባት ፡ አለው ።

18 ፤ ብዙ ፡ ሕብር ፡ ያለውንም ፡ ልብስ ፡ ለብሳ ፡ ነበር ፥ እንዲህ ፡ ያለውን ፡ ልብስ ፡ የንጉሡ ፡ ልጆች ፡ ደናግሉ ፡
ይለብሱ ፡ ነበርና ፤ አገልጋዩም ፡ አስወጥቶ ፡ በሩን ፡ ዘጋባት ።

19 ፤ ትዕማርም ፡ በራሷ ፡ ላይ ፡ ዐመድ ፡ ነስንሳ ፥ ብዙ ፡ ሕብርም ፡ ያለውን ፡ ልብሷን ፡ ተርትራ ፥ እጇንም ፡ በራሷ ፡ ላይ ፡
ጭና ፡ እየጮኸች ፡ ኼደች ።

20 ፤ ወንድሟም ፡ አቤሴሎም ፦ ወንድምሽ ፡ አምኖን ፡ ከአንቺ ፡ ጋራ ፡ ነበረን ፧ እኅቴ ፡ ሆይ ፥ አኹን ፡ ግን ፡ ዝም ፡
በዪ ፤ ወንድምሽ ፡ ነው ፤ ይህን ፡ ነገር ፡ በልብሽ ፡ አትያዢው ፡ አላት ። ትዕማርም ፡ በወንድሟ ፡ በአቤሴሎም ፡ ቤት ፡
ብቻዋን ፡ ተቀመጠች ።

21 ፤ ንጉሡም ፡ ዳዊት ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ዂሉ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ እጅግ ፡ ተቈጣ ፤ ነገር ፡ ግን ፥ የበኵር ፡ ልጁ ፡ ነበረና ፡ ስለ ፡
ወደደው ፡ የልጁን ፡ የአምኖን ፡ ነፍስ ፡ አላሳዘነም ።

22 ፤ አቤሴሎምም ፡ እኅቱን ፡ ትዕማርን ፡ ስላሳፈራት ፡ አምኖንን ፡ ጠልቶታልና ፡ አቤሴሎም ፡ አምኖንን ፡ ክፉም ፡ ኾነ ፡
መልካምም ፡ አልተናገረውም ።

23 ፤ ከኹለት ፡ ዓመትም ፡ በኋላ ፡ አቤሴሎም ፡ በኤፍሬም ፡ አቅራቢያ ፡ ባለችው ፡ በቤላሶር ፡ በጎቹን ፡
አሸለተ ፤ አቤሴሎምም ፡ የንጉሡን ፡ ልጆች ፡ ዂሉ ፡ ጠራ ።

24 ፤ አቤሴሎምም ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ መጥቶ ፦ እንሆ ፥ ባሪያኽ ፡ በጎቹን ፡ ያሸልታል ፤ ንጉሡና ፡ ሎሌዎቹ ፡ ከባሪያኽ ፡
ጋራ ፡ ይኺዱ ፡ አለው ።

25 ፤ ንጉሡም ፡ አቤሴሎምን ፦ ልጄ ፡ ሆይ ፥ እንከብድብኻለንና ፡ ዂላችን ፡ እንመጣ ፡ ዘንድ ፡ አይኾንም ፡
አለው ። የግድም ፡ አለው ፥ ርሱ ፡ ግን ፡ መረቀው ፡ እንጂ ፡ ለመኼድ ፡ እንቢ ፡ አለ ።

26 ፤ አቤሴሎምም ፦ አንተ ፡ እንቢ ፡ ካልኽ ፡ ወንድሜ ፡ አምኖን ፡ ከእኛ ፡ ጋራ ፡ እንዲኼድ ፡ እለምንኻለኹ ፡
አለ ። ንጉሡም ፦ ከአንተ ፡ ጋራ ፡ ለምን ፡ ይኼዳል ፧ አለው ።

27 ፤ አቤሴሎምም ፡ የግድ ፡ አለው ፥ አምኖንንና ፡ የንጉሡንም ፡ ልጆች ፡ ዂሉ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ሰደደ ።

28 ፤ አቤሴሎምም ፡ እንደ ፡ ንጉሥ ፡ ግብዣ ፡ ያለ ፡ ግብዣ ፡ አደረገ ፤ አቤሴሎምም ፡ አገልጋዮቹን ፦ አምኖን ፡ የወይን ፡
ጠጅ ፡ ጠጥቶ ፡ ልቡን ፡ ደስ ፡ ባለው ፡ ጊዜ ፡ እዩ ። አምኖንን ፡ ግደሉ ፡ ባልኋችኹም ፡ ጊዜ ፡
ግደሉት ፥ አትፍሩም ፤ ያዘዝኋችኹም ፡ እኔ ፡ ነኝና ፡ በርቱ ፡ ጽኑም ፡ ብሎ ፡ አዘዛቸው ።

29 ፤ የአቤሴሎም ፡ አገልጋዮች ፡ አቤሴሎም ፡ እንዳዘዛቸው ፡ በአምኖን ፡ ላይ ፡ አደረጉበት ። የንጉሡም ፡ ልጆች ፡ ዂሉ ፡
ተነሥተው ፡ በየበቅሎዎቻቸው ፡ ተቀምጠው ፡ ሸሹ ።

30 ፤ ገናም ፡ በመንገድ ፡ ሲኼዱ ፡ ለዳዊት ፦ አቤሴሎም ፡ የንጉሡን ፡ ልጆች ፡ ዂሉ ፡ ገድሏል ፥ ከነርሱም ፡ አንድ ፡
አልቀረም ፡ የሚል ፡ ወሬ ፡ መጣለት ።

31 ፤ ንጉሡም ፡ ተነሥቶ ፡ ልብሱን ፡ ቀደደ ፥ በምድር ፡ ላይም ፡ ወደቀ ፤ ባሪያዎቹም ፡ ዂሉ ፡ ልብሳቸውን ፡ ቀደው ፡

በአጠገቡ ፡ ቆሙ ።

32 ፤ የዳዊትም ፡ ወንድም ፡ የሳምዓ ፡ ልጅ ፡ ኢዮናዳብ ፦ ጌታዬ ፡ ጕልማሳዎቹ ፡ የንጉሡ ፡ ልጆች ፡ ኹሉ ፡ እንደ ፡ ሞቱ ፡
አያስብ ፤ እኅቱን ፡ ትዕማርን ፡ በግድ ፡ ካስነወራት ፡ ዠምሮ ፡ በአቤሴሎም ፡ ዘንድ ፡ የተቈረጠ ፡ ነገር ፡ ነበረና ፡ የሞተ ፡
አምኖን ፡ ብቻ ፡ ነው ።

33 ፤ አኹንም ፡ የሞተ ፡ አምኖን ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የንጉሥ ፡ ልጆች ፡ ኹሉ ፡ ሞቱ ፡ ብሎ ፡ ጌታዬ ፡ ንጉሡ ፡ ይህን ፡
ነገር ፡ በልቡ ፡ አያኑር ፡ አለው ።

34 ፤ አቤሴሎምም ፡ ኰበለለ ። ጕበኛውም ፡ ጕልማሳ ፡ ዐይኑን ፡ ከፍ ፡ አደረገ ፥ እንሆም ፥ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ በኋላው ፡
በተራራው ፡ አጠገብ ፡ በመንገድ ፡ ሲመጡ ፡ አየ ።

35 ፤ ኢዮናዳብም ፡ ንጉሡን ፦ እንሆ ፥ የንጉሡ ፡ ልጆች ፡ መጥተዋል ፤ ባሪያኽ ፡ እንዳለው ፡ እንዲሁ ፡ ኾኗል ፡ አለው ።

36 ፤ ተናግሮም ፡ በጨረሰ ፡ ጊዜ ፥ እንሆ ፥ ወዲያው ፡ የንጉሥ ፡ ልጆች ፡ ገቡ ፥ ድምፃቸውንም ፡ ከፍ ፡ አድርገው ፡
አለቀሱ ፤ ደግሞ ፡ ንጉሡና ፡ ባሪያዎቹ ፡ ኹሉ ፡ እጅግ ፡ ታላቅ ፡ ልቅሶ ፡ አለቀሱ ።

37 ፤ አቤሴሎም ፡ ግን ፡ ኰብሎ ፡ ወደጌሹር ፡ ንጉሥ ፡ ወደዐሚሁድ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ተልማይ ፡ ኼደ ። ዳዊትም ፡
ኹልጊዜ ፡ ለልጁ ፡ ያለቅስ ፡ ነበር ።

38 ፤ አቤሴሎም ፡ ኰብሎ ፡ ወደ ፡ ጌሹር ፡ ኼደ ፥ በዚያም ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ያኽል ፡ ተቀመጠ ።

39 ፤ ንጉሡም ፡ ዳዊት ፡ ስለ ፡ አምኖን ፡ ሞት ፡ ተጽናንቶ ፡ ወደ ፡ አቤሴሎም ፡ ይኼድ ፡ ዘንድ ፡ እጅግ ፡ ናፈቀ ።

____________________መጽሐፈ ፡ ሳሙኤል ፡ ካልዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 14 ። ____________________

ምዕራፍ ፡ 14 ።

1 ፤ የጽሩያም ፡ ልጅ ፡ ኢዮአብ ፡ የንጉሡ ፡ ልብ ፡ ወደ ፡ አቤሴሎም ፡ እንዳዘነበለ ፡ ዐወቀ ።

2 ፤ ኢዮአብም ፡ ወደ ፡ ቴቁሔ ፡ ልኮ ፡ ከዚያ ፡ ብልኀተኛ ፡ ሴት ፡ አስመጣና ፦ አልቅሺ ፥ የሐዘንም ፡ ልብስ ፡
ልበሺ ፥ ዘይትም ፡ አትቀቢ ፥ ስለ ፡ ሞተ ፡ ሰውም ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ እንደምታለቅሺ ፡ ኹኚ ፤

3 ፤ ወደ ፡ ንጉሡም ፡ ግብተሽ ፡ እንዲህ ፡ ያለውን ፡ ቃል ፡ ንገሪው ፡ አላት ፤ ኢዮአብም ፡ ቃሉን ፡ በርሷ ፡ አፍ ፡ አደረገ ።

4 ፤ እንዲሁም ፥ የቴቁሔዪቱ ፡ ሴት ፡ ወደ ፡ ንጉሥ ፡ ገብታ ፡ በግንባሯ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ወደቀች ፥ እጅ ፡
ነሥታም ፦ ንጉሥ ፡ ሆይ ፥ አድነኝ ፡ አለች ።

5 ፤ ንጉሡም ፦ ምን ፡ ኾነሻል ፥ አላት ። ርሷም ፡ መልሳ ፡ አለች ፦ በእውነት ፡ እኔ ፡ ባሌ ፡ የሞተብኝ ፡ ባልቴት ፡ ሴት ፡
ነኝ ።

6 ፤ ለኔም ፡ ለባሪያኽ ፡ ኹለት ፡ ወንዶች ፡ ልጆች ፡ ነበሩኝ ፥ በሜዳም ፡ ተጣሉ ፤ የሚገላግላቸውም ፡
አልነበረም ፥ አንዱም ፡ ሌላውን ፡ መቶ ፡ ገደለው ።

7 ፤ እንሆም ፥ ዘመዶች ፡ ኹሉ ፡ በባሪያኽ ፡ ላይ ፡ ተነሥተው ፦ ስለገደለው ፡ ስለወንድሙ ፡ ነፍስ ፡ እንገድለው ፡ ዘንድ ፡
ወንድሙን ፡ የገደለውን ፡ አውጪ ፡ አሉኝ ፤ እንዲሁም ፡ ደግሞ ፡ ወራሹን ፡ የቀረውን ፡ መብራቴን ፡ ያጠፋሉ ፥ የባሌን ፡
ስምና ፡ ዘርም ፡ ከምድር ፡ ላይ ፡ አያስቀሩም ።

8 ፤ ንጉሡም ፡ ሴቲቱን ፦ ወደ ፡ ቤትሽ ፡ ኺጂ ፥ እኔም ፡ ስለ ፡ አንቺ ፡ አዛለኹ ፡ አላት ።

9 ፤ የቴቁሔዪቱም ፡ ሴት ፡ ንጉሡን ፦ ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ፥ ኀጢአቱ ፡ በእኔና ፡ በአባቴ ፡ ቤት ፡ ላይ ፡
ይኹን ፤ ንጉሡና ፡ ዙፋኑ ፡ ንጹሕ ፡ ይኹን ፡ አለችው ።

10 ፤ ንጉሡም ፦ የሚናገርሽን ፡ አምጪልኝ ፥ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ደግሞ ፡ አይነካሽም ፡ አለ ።

11 ፤ ርሷም ፦ ደም ፡ ተበቃዮችም ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ እንዳያጠፉ ፡ ልጄንም ፡ እንዳይገድሉ ፥ ንጉሡ ፡ አምላኩን ፡
እግዚአብሔርን ፡ ያስብ ፡ አለች ። ርሱም ፦ ሕያው ፡ እግዚአብሔርን! ከልጅሽ ፡ አንድ ፡ ጠጕር ፡ በምድር ፡ ላይ ፡
አይወድቅም ፡ አለ ።

12 ፤ ሴቲቱም ፦ እኔ ፡ ባሪያኽ ፡ ለጌታዬ ፡ ለንጉሥ ፡ አንድ ፡ ቃል ፡ ልናገር ፡ አለች ፤ ርሱም ፦ ተናገሪ ፡ አለ ።

13 ፤ ሴቲቱም ፡ አለች ፦ በእግዚአብሔር ፡ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ዐሰብኽ ፧ ንጉሡ ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ተናግሯልና ፡ ያሳደደውን ፡ ስላላስመለሰ ፡ በደለኛ ፡ ነው ።

14 ፤ ኹላችን ፡ እንሞታለን ፥ በምድርም ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ፈሰሰና ፡ እንደማይመለስ ፡ ውሃ ፡ ነን ፤ እግዚአብሔርም ፡ የነፍስን ፡ ጥፋት ፡ አይወድም ፥ ነገር ፡ ግን ፥ የተጣለ ፡ ሰው ፡ ፈጽሞ ፡ እንዳይጠፋ ፡ በምክሩ ፡ ያስባል ።

15 ፤ አኹንም ፡ ሕዝቡ ፡ ስለሚያስፈራኝ ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ለጌታዬ ፡ ለንጉሥ ፡ እነግረው ፡ ዘንድ ፡ መጥቻለኹ ፤ እኔም ፡ ባሪያኽ ፦ ምናልባት ፡ የእኔን ፡ የባሪያውን ፡ ልመና ፡ ንጉሡ ፡ ያደርግልኝ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ ለንጉሡ ፡ ልናገር ፤

16 ፤ ርሷንና ፡ ልጇን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ርስት ፡ ያጠፉቸው ፡ ዘንድ ፡ ከሚሿ ፡ ሰው ፡ እጅ ፡ ያድን ፡ ዘንድ ፡ ንጉሡ ፡ ባሪያውን ፡ ይሰማል ፡ አልኹ ።

17 ፤ እኔም ፡ ባሪያኽ ፦ መልካሙንና ፡ ክፉውን ፡ ነገር ፡ ለመስማት ፡ ንጉሡ ፡ ጌታዬ ፡ እንደእግዚአብሔር ፡ መልአክ ፡ ነውና ፥ የጌታዬ ፡ የንጉሡ ፡ ቃል ፡ ያጽናናኛል ፤ አምላክኽም ፡ እግዚአብሔር ፡ ከአንተ ፡ ጋራ ፡ ይኹን ፡ አልኹ ።

18 ፤ ንጉሡም ፡ ለሴቲቱ ፡ መልሶ ፦ የምጠይቅሽን ፡ ነገር ፡ አትሰውሪኝ ፡ አላት ። ሴቲቱም ፦ ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡ ይናገር ፡ አለች ።

19 ፤ ንጉሡም ፦ በዚህ ፡ ኹሉ ፡ የኢዮአብ ፡ እጅ ፡ ከአንቺ ፡ ጋራ ፡ ነውን ፧ አላት ። ሴቲቱም ፡ መልሳ ፦ ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ፥ በሕያው ፡ ነፍስኽ ፡ እምላለኹ! ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡ ከተናገረው ፡ ነገር ፡ ኹሉ ፡ ወደ ፡ ቀኝም ፡ ወደ ፡ ግራም ፡ ሊል ፡ የሚችል ፡ የለም ፤ ባሪያኽ ፡ ኢዮአብ ፡ አዘኛል ፥ ይህንም ፡ ቃል ፡ ኹሉ ፡ በባሪያኽ ፡ አፍ ፡ አደረገው ።

20 ፤ ባሪያኽ ፡ ኢዮአብ ፡ የዚህ ፡ ነገር ፡ መልክ ፡ እንዲለወጥ ፡ አደረገ ፤ ነገር ፡ ግን ፥ የእግዚአብሔር ፡ መልአክ ፡ ጠቢብ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፥ አንተም ፡ ጌታዬ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ ነገር ፡ ኹሉ ፡ ታውቅ ፡ ዘንድ ፡ ጠቢብ ፡ ነኽ ፡ አለች ።

21 ፤ ንጉሡም ፡ ኢዮአብን ፦ እንሆ ፥ ይህን ፡ ነገር ፡ አድርጌያለኹ ፤ እንግዲህ ፡ ኺድና ፡ ብላቴናውን ፡ አቤሴሎምን ፡ መልሰው ፡ አለው ።

22 ፤ ኢዮአብም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ በግንባሩ ፡ ወድቆ ፡ እጅ ፡ ነሣ ፥ ንጉሡንም ፡ ባረከ ፤ ኢዮአብም ፦ ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ፥ የባሪያኽን ፡ ነገር ፡ አድርገኻልና ፡ በዐይንኽ ፡ ፊት ፡ ሞገስ ፡ እንዳገኘ ፡ ባሪያኽ ፡ ዛሬ ፡ ዐወቀ ፡ አለ ።

23 ፤ ኢዮአብም ፡ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡ ጌሹር ፡ ኼደ ፥ አቤሴሎምንም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ይዞ ፡ መጣ ።

24 ፤ ንጉሡም ፦ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ይኺድ ፡ እንጂ ፡ ፊቴን ፡ እንዳያይ ፡ አለ ፤ አቤሴሎምም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ኼደ ፥ የንጉሡንም ፡ ፊት ፡ አላየም ።

25 ፤ በእስራኤልም ፡ ኹሉ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ አቤሴሎም ፡ በውበቱ ፡ የተመሰገነ ፡ ሰው ፡ አልነበረም ፤ ከእግሩ ፡ እስከ ፡ ራሱ ፡ ድረስ ፡ ነውር ፡ አልነበረበትም ።

26 ፤ ጠጕሩም ፡ ይከብደው ፡ ነበርና ፥ በዓመት ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ይቈርጠው ፡ ነበር ፤ ሲቈረጥም ፡ የራሱ ፡ ጠጕር ፡ በንጉሥ ፡ ሚዛን ፡ ኹለት ፡ መቶ ፡ ሰቅል ፡ ያኽል ፡ ይመዝን ፡ ነበር ።

27 ፤ ለአቤሴሎምም ፡ ሦስት ፡ ወንዶች ፡ ልጆችና ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ተወለዱለት ፤ የሴቲቱም ፡ ልጅ ፡ ስም ፡ ትዕማር ፡ ነበረ ፥ ርሷም ፡ የተዋበች ፡ ሴት ፡ ነበረች ።

28 ፤ አቤሴሎምም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ኹለት ፡ ዓመት ፡ ሙሉ ፡ የንጉሡን ፡ ፊት ፡ ሳያይ ፡ ተቀመጠ ።

29 ፤ አቤሴሎምም ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ይልከው ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ኢዮአብ ፡ ላከ ፥ ወደ ፡ ርሱም ፡ ሊመጣ ፡ አልወደደም ፤ ኹለተኛም ፡ ላከበት ፥ ሊመጣ ፡ ግን ፡ አልወደደም ።

30 ፤ ባሪያዎቹንም ፦ በዕርሻዬ ፡ አጠገብ ፡ ያለውን ፡ የኢዮአብን ፡ ዕርሻ ፡ እዩ ፥ በዚያም ፡ ገብስ ፡ አለው ፤ ኺዳችኹ ፡ በእሳት ፡ አቃጥሉት ፡ አላቸው ። የአቤሴሎምም ፡ ባሪያዎች ፡ ዕርሻውን ፡ አቃጠሉት ።

31 ፤ ኢዮአብም ፡ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡ አቤሴሎም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ መጣና ፦ ባሪያዎችኽ ፡ ዕርሻዬን ፡ ስለ ፡ ምን ፡ አቃጠሉት ፧ አለው ።

32 ፤ አቤሴሎምም ፡ ኢዮአብን ፡ መልሶ ፦ ከጌሹር ፡ ለምን ፡ መጣኹ ፥ በዚያም ፡ ተቀምጬ ፡ ብኾን ፡ ይሻለኝ ፡ ነበር ፡ ብለኽ ፡ እንድትነግረው ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ እልክኽ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ጠራኹኽ ፤ አኹንም ፡ የንጉሡን ፡ ፊት ፡ ልይ ፥ ኀጢአት ፡ ቢኾንብኝ ፡ ይግደለኝ ፡ አለው ።

33 ፤ ኢዮአብም ፡ ወደ ፡ ንጉሥ ፡ መጥቶ ፡ ነገረው ፤ አቤሴሎምንም ፡ ጠራው ፥ ወደ ፡ ንጉሡም ፡ ገብቶ ፡ በንጉሥ ፡ ፊት ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ በግንባሩ ፡ ተደፋ ፤ ንጉሡም ፡ አቤሴሎምን ፡ ሳመው ።

## መጽሐፈ ፡ ሳሙኤል ፡ ካልዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 15 ።

ምዕራፍ ፡ 15 ።

1 ፤ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ አቤሴሎም ፡ ሠረገላና ፡ ፈረሶች ፥ በፊቱም ፡ የሚሮጡ ፡ ዐምሳ ፡ ሰዎች ፡ አዘጋጀ ።

2 ፤ አቤሴሎምም ፡ በማለዳ ፡ ተነሥቶ ፡ በበሩ ፡ አደባባይ ፡ ይቆም ፡ ነበር ፤ አቤሴሎምም ፡ ከንጉሥ ፡ ለማስፈረድ ፡ ጕዳይ ፡ የነበረውን ፡ ኹሉ ፡ ወደ ፡ ርሱ ፡ እየጠራ ፦ አንተ ፡ ከወዴት ፡ ከተማ ፡ ነኽ ፥ ብሎ ፡ ይጠይቅ ፡ ነበር ። ርሱም ፦ እኔ ፡ ባሪያኽ ፡ ከእስራኤል ፡ ነገድ ፡ ከአንዲቱ ፡ ነኝ ፡ ብሎ ፡ ይመልስ ፡ ነበር ።

3 ፤ አቤሴሎምም ፦ ነገርኽ ፡ እውነትና ፡ ቅን ፡ ነው ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ከንጉሥ ፡ ታዞ ፡ የሚሰማኽ ፡ የለም ፡ ይለው ፡ ነበር ።

4 ፤ አቤሴሎምም ፦ ነገርና ፡ ክርክር ፡ ያለው ፡ ኹሉ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ይመጣ ፡ ዘንድ ፡ ቅንም ፡ ፍርድ ፡ እፈርድለት ፡ ዘንድ ፡ በአገር ፡ ላይ ፡ ፈራጅ ፡ አድርጎ ፡ ማን ፡ በሾመኝ ፥ ይል ፡ ነበር ።

5 ፤ ሰውም ፡ እጅ ፡ ሊነሣው ፡ ወደ ፡ ርሱ ፡ በቀረበ ፡ ጊዜ ፡ እጁን ፡ ዘርግቶ ፡ ይይዝና ፡ ይስመው ፡ ነበር ።

6 ፤ እንዲሁም ፡ አቤሴሎም ፡ ከንጉሥ ፡ ፍርድ ፡ ሊሰማ ፡ ከእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ በሚመጣ ፡ ኹሉ ፡ ያደርግ ፡ ነበር ፤ አቤሴሎምም ፡ የእስራኤልን ፡ ሰዎች ፡ ልብ ፡ ሰረቀ ።

7 ፤ እንዲህም ፡ ኾነ ፤ ከአራት ፡ ዓመት ፡ በኋላ ፡ አቤሴሎም ፡ ንጉሡን ፦ ለእግዚአብሔር ፡ የተሳልኹትን ፡ ስእለት ፡ ለመስጠት ፡ ወደ ፡ ኬብሮን ፥ እባክኽ ፥ ልኺድ ።

8 ፤ እኔ ፡ ባሪያኽ ፡ በሶርያ ፡ ጌሹር ፡ ሳለኹ ፦ እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ቢመልሰኝ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መሥዋዕት ፡ አቀርባለኹ ፡ ብዬ ፡ ስእለት ፡ ተስዬ ፡ ነበር ፡ አለው ።

9 ፤ ንጉሡም ፦ በደኅና ፡ ኺድ ፡ አለው ፤ ተነሥቶም ፡ ወደ ፡ ኬብሮን ፡ ኼደ ።

10 ፤ አቤሴሎምም ፡ በእስራኤል ፡ ነገድ ፡ ኹሉ ፦ የቀንደ ፡ መለከት ፡ ድምፅ ፡ በሰማችኹ ፡ ጊዜ ፦ አቤሴሎም ፡ በኬብሮን ፡ ነገሠ ፡ በሉ ፡ የሚሉ ፡ ጕበኛዎች ፡ ላከ ።

11 ፤ የተጠሩትም ፡ ኹለት ፡ መቶ ፡ ሰዎች ፡ ከአቤሴሎም ፡ ጋራ ፡ በየዋህነት ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ኼዱ ፤ የሚኾነውንም ፡ ነገር ፡ ከቶ ፡ አያውቁም ፡ ነበር ።

12 ፤ አቤሴሎምም ፡ የዳዊት ፡ መካር ፡ የነበረውን ፡ የጊሎ ፡ ሰው ፡ አኪጦፌልን ፡ ከከተማው ፡ ከጊሎ ፡ መሥዋዕት ፡ በሚያቀርብበት ፡ ጊዜ ፡ አስጠራው ። ሤራውም ፡ ጽኑ ፡ ኾነ ፤ ከአቤሴሎምም ፡ ጋራ ፡ ያለ ፡ ሕዝብ ፡ እየበዛ ፡ ኼደ ።

13 ፤ ለዳዊትም ፦ የእስራኤል ፡ ሰዎች ፡ ልብ ፡ ከአቤሴሎም ፡ ጋራ ፡ ኾኗል ፡ የሚል ፡ ወሬኛ ፡ መጣለት ።

14 ፤ ዳዊትም ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ያሉትን ፡ ባሪያዎቹን ፡ ኹሉ ፦ ተነሡ ፥ እንሽሽ ፡ ያለዚያ ፡ ከአቤሴሎም ፡ እጅ ፡ የሚድን ፡ ከእኛ ፡ የለምና ፤ መጥቶም ፡ እንዳይዘን ፥ ክፉም ፡ እንዳያመጣብን ፡ ከተማዪቱንም ፡ በሰይፍ ፡ ስለት ፡ እንዳይመታ ፡ ፈጥናችኹ ፡ እንኺድ ፡ አላቸው ።

15 ፤ የንጉሡም ፡ ባሪያዎች ፡ ንጉሡን ፦ እንሆ ፥ ጌታችን ፡ ንጉሡ ፡ የመረጠውን ፡ ኹሉ ፡ እኛ ፡ ባሪያዎችኽ ፡ ዕሺ ፡ ብለን ፡ እናደርጋለን ፡ አሉት ።

16 ፤ ንጉሡም ፡ ከርሱም ፡ በኋላ ፡ ቤተ ፡ ሰቡ ፡ ኹሉ ፡ ወጡ ፤ ንጉሡም ፡ ዐሥሩን ፡ ሴቶች ፡ ቁባቶቹን ፡ ቤቱን ፡ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ፡ ተወ ።

17 ፤ ንጉሡም ፡ ከርሱም ፡ በኋላ ፡ ሕዝቡ ፡ ኹሉ ፡ ወጡ ፥ በቤትሜርሐቅም ፡ ቆሙ ።

መጡ ።

12 ፤ ደግሞም ፡ አንድ ፡ ልብ ፡ ይሰጣቸው ፡ ዘንድ ፥ በእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ የኾነውን ፡ የንጉሡንና ፡ የአለቃዎቹን ፡ ትእዛዝ ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ የእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ ኾነ ።

13 ፤ በኹለተኛውም ፡ ወር ፡ የቂጣውን ፡ በዓል ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ እጅግ ፡ ታላቅ ፡ ጉባኤ ፡ የኾነ ፡ ሕዝብ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ተከማቸ ።

14 ፤ ተነሥተውም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የነበሩትን ፡ መሠዊያዎችና ፡ ለጣዖታት ፡ የሚያጥኑበትን ፡ ዕቃ ፡ ኹሉ ፡ አስወገዱ ፥ በቄድሮንም ፡ ወንዝ ፡ ጣሉት ።

15 ፤ በኹለተኛውም ፡ ወር ፡ በዐሥራ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ ፋሲካውን ፡ ዐረዱ ፤ ካህናቱና ፡ ሌዋውያኑም ፡ ዐፈሩ ፥ ተቀደሱም ፥ ወደእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ አመጡ ።

16 ፤ እንደእግዚአብሔርም ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ሙሴ ፡ ሕግ ፡ በሥርዐታቸው ፡ ቆሙ ፤ ካህናቱም ፡ ከሌዋውያን ፡ እጅ ፡ የተቀበሉትን ፡ ደም ፡ ይረጩ ፡ ነበር ።

17 ፤ በጉባኤውም ፡ ያልተቀደሱ ፡ እጅግ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ፤ ስለዚህም ፡ ሌዋውያን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ይቀድሷቸው ፡ ዘንድ ፡ ንጹሓን ፡ ላልኾኑት ፡ ኹሉ ፡ ፋሲካውን ፡ ያርዱላቸው ፡ ነበር ።

18 ፤ እንደ ፡ ትእዛዙም ፡ ሳይኾን ፡ ከኤፍሬምና ፡ ከምናሴ ፡ ከይሳኮርና ፡ ከዛብሎንም ፡ ወገን ፡ እጅግ ፡ ሰዎች ፡ ሳይነጹ ፡ ፋሲካውን ፡ በሉ ።

19 ፤ ሕዝቅያስም ፦ ምንም ፡ እንደ ፡ መቅደሱ ፡ ማንጻት ፡ ባይነጻ ፡ የአባቶቹን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለመፈለግ ፡ ልቡን ፡ የሚያቀናውን ፡ ኹሉ ፡ ቸሩ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይቅር ፡ ይበለው ፡ ብሎ ፡ ስለ ፡ እነርሱ ፡ ጸለየ ።

20 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ሕዝቅያስን ፡ ሰማው ፥ ሕዝቡንም ፡ ፈወሰ ።

21 ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ ተገኝተው ፡ የነበሩ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ የቂጣውን ፡ በዓል ፡ በታላቅ ፡ ደስታ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ አደረጉ ፤ ሌዋውያኑና ፡ ካህናቱም ፡ በዜማ ፡ ዕቃ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እየዘመሩ ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመሰግኑ ፡ ነበር ።

22 ፤ ሕዝቅያስም ፡ በእግዚአብሔር ፡ አገልግሎት ፡ አስተዋዮች ፡ የነበሩትን ፡ ሌዋውያንን ፡ ኹሉ ፡ ያጽናና ፡ ነበር ። የደኅንነትንም ፡ መሥዋዕት ፡ እያቀረቡ ፥ የአባቶቻቸውንም ፡ አምላክ ፡ እያመሰገኑ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ በዓል ፡ አደረጉ ።

23 ፤ 24 ፤ የይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ ሕዝቅያስ ፡ ስለ ፡ ቍርባን ፡ ሺሕ ፡ ወይፈኖችና ፡ ሰባት ፡ ሺሕ ፡ በጎች ፡ ለጉባኤው ፡ ሰጥቶ ፡ ነበርና ፥ አለቃዎቹም ፡ ሺሕ ፡ ወይፈኖችና ፡ ዐሥር ፡ ሺሕ ፡ በጎች ፡ ለጉባኤው ፡ ሰጥተው ፡ ነበርና ፥ ከካህናቱም ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ተቀድሰው ፡ ነበርና ፥ ጉባኤው ፡ ኹሉ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ በዓል ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ተማከሩ ፤ በደስታም ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ በዓል ፡ አደረጉ ።

25 ፤ የይሁዳም ፡ ጉባኤ ፡ ኹሉ ፥ ካህናቱና ፡ ሌዋውያኑ ፥ ከእስራኤልም ፡ የመጡ ፡ ጉባኤ ፡ ኹሉ ፥ ከእስራኤልም ፡ አገር ፡ የመጡትና ፡ በይሁዳ ፡ የኖሩት ፡ እንግዳዎች ፡ ደስ ፡ አላቸው ።

26 ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ ታላቅ ፡ ደስታ ፡ ኾነ ፤ ከእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ከዳዊት ፡ ልጅ ፡ ከሰሎሞን ፡ ዘመን ፡ ዠምሮ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ በዓል ፡ በኢየሩሳሌም ፡ አልተደረገም ፡ ነበር ።

27 ፤ ካህናቱና ፡ ሌዋውያኑም ፡ ተነሥተው ፡ ሕዝቡን ፡ ባረኩ ፤ ድምፃቸውም ፡ ተሰማ ፥ ጸሎታቸውም ፡ ወደ ፡ ቅዱስ ፡ መኖሪያው ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ዐረገ ።

መጽሐፈ ፡ ዜና ፡ መዋዕል ፡ ካልዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 31 ።

ምዕራፍ ፡ 31 ፤

1 ፤ ይህም ፡ ኹሉ ፡ በተፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ በዚያ ፡ የተገኙ ፡ እስራኤል ፡ ኹሉ ፡ ወደይሁዳ ፡ ከተማዎች ፡ ወጥተው ፡ ኹሉን ፡ ፈጽመው ፡ እስካጠፏቸው ፡ ድረስ ፡ ሐውልቶቹን ፡ ሰባበሩ ፥ የማምለኪያ ፡ ዐጸዶቹንም ፡ ቈረጡ ፥ በይሁዳና ፡ በብንያምም ፡ ኹሉ ፡ ደግሞም ፡ በኤፍሬምና ፡ በምናሴ ፡ የነበሩትን ፡ የኰረብታው ፡ መስገጃዎችና ፡ መሠዊያዎች ፡

አፈረሱ ። የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ኹሉ ፡ ወደ ፡ ርስታቸውና ፡ ወደ ፡ ከተማዎቻቸው ፡ ተመለሱ ።

2 ፤ ሕዝቅያስም ፡ የካህናትንና ፡ የሌዋውያንን ፡ ሰሞን ፡ በየክፍላቸውና ፡ በያገልግሎታቸው ፡ አቆመ ፤ በእግዚአብሔር ፡
ቤት ፡ አደባባይ ፡ በሮች ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕትና ፡ የደኅንነቱን ፡ መሥዋዕት ፡ ያቀርቡ ፡ ዘንድ ፥ ያገለግሉም ፡
ዘንድ ፥ ያመሰግኑም ፡ ያከብሩም ፡ ዘንድ ፡ ካህናቱንና ፡ ሌዋውያኑን ፡ አቆመ ።

3 ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ሕግ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ በጧትና ፡ በማታ ፥ በሰንበታቱም ፥ በመባቻዎቹም ፥ በበዓላትም ፡
ለሚቀርበው ፡ ለሚቃጠለው ፡ መሥዋዕት ፡ ንጉሡ ፡ ከገንዘቡ ፡ የሚከፍለውን ፡ ወሰነ ።

4 ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ ለአገልግሎት ፡ እንዲጸኑ ፡ ለካህናቱና ፡ ለሌዋውያን ፡ ክፍላቸውን ፡ ይሰጡ ፡ ዘንድ ፡
በኢየሩሳሌም ፡ የሚኖሩትን ፡ ሕዝብ ፡ አዘዘ ።

5 ፤ ይህንም ፡ ነገር ፡ እንዳዘዘ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ የእኽሉንና ፡ የወይኑን ፡ ጠጅ ፡ የዘይቱንና ፡
የማሩንም ፥ የዕርሻውንም ፡ ፍሬ ፡ ኹሉ ፡ በኵራት ፡ ሰጡ ፤ የኹሉንም ፡ ዓሥራት ፡ አብዝተው ፡ አቀረቡ ።

6 ፤ በይሁዳም ፡ ከተማዎች ፡ የሚኖሩ ፡ የእስራኤልና ፡ የይሁዳ ፡ ልጆች ፡ የበሬውንና ፡ የበጉን ፡
ዓሥራት ፥ ለአምላካቸውም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የተቀደሰውን ፡ ዓሥራት ፡ አመጡ ፥ ከምረውም ፡ አኖሩት ።

7 ፤ በሦስተኛው ፡ ወር ፡ መከመር ፡ ዠመሩ ፤ በሰባተኛውም ፡ ወር ፡ ጨረሱ ።

8 ፤ ሕዝቅያስና ፡ አለቃዎቹም ፡ መጥተው ፡ ክምሩን ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔርና ፡ ሕዝቡን ፡ እስራኤልን ፡ ባረኩ ።

9 ፤ ሕዝቅያስም ፡ ካህናቱንና ፡ ሌዋውያኑን ፡ ስለ ፡ ክምሩ ፡ ጠየቀ ።

10 ፤ ከሳዶቅም ፡ ወገን ፡ የኾነ ፡ ዋነኛው ፡ ካህን ፡ ዓዛሪያስ ፦ ሕዝቡ ፡ ቍርባኑን ፡ ወደእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ማቅረብ ፡
ከዠመረ ፡ ወዲህ ፡ በልተናል ፥ ጠግበናልም ፥ እግዚአብሔር ፡ ሕዝቡን ፡ ባርኳልና ፥ ብዙ ፡ ተርፏል ፤ የተረፈውም ፡ ይህ ፡
ክምር ፡ ትልቅ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ተናገረ ።

11 ፤ ሕዝቅያስም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ጐተራ ፡ ያዘጋጁ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፤ እነርሱም ፡ አዘጋጁ ።

12 ፤ ቍርባኑና ፡ ዓሥራቱን ፡ የተቀደሱትንም ፡ በእምነት ፡ ወደዚያ ፡ አገቡት ። ሌዋዊውም ፡ ኮናንያ ፡
ተሾመባቸው ፥ ወንድሙም ፡ ሰሜኢ ፡ በማዕርግ ፡ ኹለተኛ ፡ ነበረ ፤

13 ፤ በንጉሡም ፡ በሕዝቅያስና ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አለቃ ፡ በዐዛርያስ ፡ ትእዛዝ ፡
ይሒዒል ፥ ዓዛዝያ ፥ ናሖት ፥ ዐሳሄል ፥ ይሬሞት ፥ ዮዛባት ፥ ኤሊኤል ፥ ሰማክያ ፥ መሐት ፥ በናያስ ፥ ከኮናንያና ፡
ከወንድሙ ፡ ከሰሜኢ ፡ እጅ ፡ በታች ፡ ተቈጣጣሪዎች ፡ ነበሩ ።

14 ፤ የሌዋዊውም ፡ የይምና ፡ ልጅ ፡ የምሥራቁ ፡ ደጅ ፡ በረኛ ፡ ቆሬ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መባና ፡ የተቀደሱትን ፡ ነገሮች ፡
እንዲያካፍል ፡ ሕዝቡ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በፈቃድ ፡ ባቀረቡት ፡ ላይ ፡ ተሾመ ።

15 ፤ በካህናቱም ፡ ከተማዎች ፡ ለታላላቆችና ፡ ለታናናሾች ፡ ወንድሞቻቸው ፡ በየሰሞናቸው ፡ ክፍላቸውን ፡ በእምነት ፡
ይሰጡ ፡ ዘንድ ፡ ዔዴን ፥ ሚንያሚን ፥ ኢያሱ ፥ ሸማያ ፥ አማርያ ፥ ሴኬንያ ፡ ከእጁ ፡ በታች ፡ ነበሩ ።

16 ፤ ከሦስትም ፡ ዓመት ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ላሉ ፡ በየሰሞናቸው ፡ ለሥራቸውና ፡ ለአገልግሎታቸው ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡
ወደእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ለሚገቡ ፡ ወንዶች ፡ ኹሉ ፤

17 ፤ በያባቶቻቸውም ፡ ቤት ፡ ለተቈጠሩ ፡ ካህናት ፥ ከኻያ ፡ ዓመትም ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ላሉ ፡ በየሥርዐታቸውና ፡
በየሰሞናቸው ፡ ለተቈጠሩ ፡ ሌዋውያን ፥

18 ፤ በማኅበሩም ፡ ኹሉ ፡ በየትውልዳቸው ፡ ለተቈጠሩ ፡ ለሕፃናታቸውና ፡ ለሚስቶቻቸው ፡ ለወንዶችና ፡ ለሴቶች ፡
ልጆቻቸውም ፡ ይሰጡ ፡ ነበር ፤ በእምነት ፡ ተቀድሰዋልና ።

19 ፤ በየከተማዪቱም ፡ ኹሉ ፡ በከተማቸው ፡ መሰምሪያዎቹ ፡ ላሉ ፡ ለአሮን ፡ ልጆች ፡ ለካህናቱ ፥ ከካህናቱም ፡ ወገን ፡
ላሉ ፡ ወንዶች ፡ ኹሉ ፥ በትውልዳቸውም ፡ ለተቈጠሩ ፡ ሌዋውያን ፡ ኹሉ ፡ ክፍላቸውን ፡ ይሰጡ ፡ ዘንድ ፡ በስማቸው ፡
የተጻፉ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ።

20 ፤ ሕዝቅያስም ፡ በይሁዳ ፡ ኹሉ ፡ እንዲህ ፡ አደረገ ፤ በአምላኩም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ መልካምንና ፡ ቅንን ፡

ነገር ፡ እውነትንም ፡ አደረገ ።

21 ፤ ስለእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ አገልግሎት ፡ በጀመረው ፡ ሥራ ፡ ኹሉ ፥ በሕጉና ፡ በትእዛዙም ፥ አምላኩን ፡
ለመፈለግ ፡ በፍጹም ፡ ልቡ ፡ አደረገው ፥ ተከናወነለትም ።

## መጽሐፈ ፡ ዜና ፡ መዋዕል ፡ ካልዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 32 ።

ምዕራፍ ፡ 32 ።

1 ፤ ከዚህም ፡ ነገርና ፡ ከዚህ ፡ እምነት ፡ በዃላ ፡ የአሶር ፡ ንጉሥ ፡ ሰናክሬም ፡ መጥቶ ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡
ገባ ፥ በተመሸጉትም ፡ ከተማዎች ፡ ፊት ፡ ሰፈረ ፥ ሊወስዳቸውም ፡ ዐሰበ ።

2 ፤ ሕዝቅያስም ፡ ሰናክሬም ፡ እንደ ፡ መጣ ፥ ኢየሩሳሌምንም ፡ ሊወጋ ፡ ፊቱን ፡ እንዳቀና ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፥

3 ፤ ከከተማዪቱ ፡ በስተውጭ ፡ ያለውን ፡ የውሃውን ፡ ምንጭ ፡ ይደፍኑ ፡ ዘንድ ፡ ከአለቃዎቹና ፡ ከኀያላኑ ፡ ጋራ ፡
ተማከረ ፤ እነርሱም ፡ ረዱት ።

4 ፤ እጅግም ፡ ሰዎች ፡ ተሰብስበው ፦ የአሶር ፡ ነገሥታት ፡ መጥተው ፡ ብዙ ፡ ውሃ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ያገኛሉ ፧ ብለው ፡
ምንጩን ፡ ኹሉ ፥ በምድርም ፡ መካከል ፡ ይጐርፍ ፡ የነበረውን ፡ ወንዝ ፡ ደፈኑ ።

5 ፤ ሰውነቱንም ፡ አጸናና ፥ የፈረሰውንም ፡ ቅጥር ፡ ኹሉ ፡ ጠገነ ፥ በላዩም ፡ ግንብ ፡ ሠራበት ፥ ከርሱም ፡ በስተውጭ ፡
ሌላ ፡ ቅጥር ፡ ሠራ ፤ በዳዊትም ፡ ከተማ ፡ ያለችውን ፡ ሚሎን ፡ አጠነከረ ፤ ብዙም ፡ መሣሪያና ፡ ጋሻ ፡ ሠራ ።

6 ፤ የጦር ፡ አለቃዎቹንም ፡ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ ሾመ ፥ ኹሉንም ፡ በከተማዪቱ ፡ በር ፡ ወዳለው ፡ አደባባይ ፡ ሰብስቦ ።

7 ፤ ጽኑ ፥ አይዟችኹ ፤ ከእኛም ፡ ጋራ ፡ ያለው ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ካለው ፡ ይበልጣልና ፥ ከአሶር ፡ ንጉሥና ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡
ካለው ፡ ጭፍራ ፡ ኹሉ ፡ አትፍሩ ፥ አትደንግጡም ።

8 ፤ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ የሥጋ ፡ ክንድ ፡ ነው ፤ ከእኛ ፡ ጋራ ፡ ያለው ፡ ግን ፡ የሚረዳንና ፡ የሚዋጋልን ፡ አምላካችን ፡
እግዚአብሔር ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ አጸናናቸው ። ሕዝቡም ፡ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በሕዝቅያስ ፡ ቃል ፡ ተጽናና ።

9 ፤ ከዚህም ፡ በዃላ ፡ የአሶር ፡ ንጉሥ ፡ ሰናክሬም ፡ ከሰራዊቱ ፡ ኹሉ ፡ ጋራ ፡ በለኪሶ ፡ ፊት ፡ ሳለ ፡ ባሪያዎቹን ፡ ወደ ፡
ኢየሩሳሌም ፡ ወደይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ ሕዝቅያስና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ወደነበሩ ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ ኹሉ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡
ላከ ።

10 ፤ የአሶር ፡ ንጉሥ ፡ ሰናክሬም ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ እናንተ ፡ በማን ፡ ተማምናችኹ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ምሽግ ፡
ትቀመጣላችኹ ፧

11 ፤ አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡ ከአሶር ፡ ንጉሥ ፡ እጅ ፡ ያድነናል ፡ እያለ ፡ በራብና ፡ በጥም ፡ እንድትሞቱ ፡ አሳልፎ ፡
ይሰጣችኹ ፡ ዘንድ ፡ የሚያባብላችኹ ፡ ሕዝቅያስ ፡ አይደለምን ፧

12 ፤ ባንድ ፡ መሠዊያ ፡ ፊት ፡ ስገዱ ፥ በርሱም ፡ ላይ ፡ ዕጠኑ ፡ እያለ ፡ ይሁዳንና ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ አዞ ፥ የኰረብታው ፡
መስገጃዎቹና ፡ መሠዊያዎቹን ፡ ያፈረሰ ፡ ይህ ፡ ሕዝቅያስ ፡ አይደለምን ፧

13 ፤ እኔና ፡ አባቶቼ ፡ በምድር ፡ አሕዛብ ፡ ኹሉ ፡ ያደረግነውን ፡ አላወቃችኹምን ፧ የምድርስ ፡ ኹሉ ፡ አሕዛብ ፡
አማልክት ፡ አገራቸውን ፡ ከእጄ ፡ ያድኑ ፡ ዘንድ ፡ በእውኑ ፡ ተቻላቸውን ፧

14 ፤ አምላካችኹስ ፡ ከእጄ ፡ እናንተን ፡ ለማዳን ፡ ይችል ፡ ዘንድ ፡ አባቶቼ ፡ ካጠፏቸው ፡ ከአሕዛብ ፡ አማልክት ፡ ኹሉ ፡
ሕዝቡን ፡ ከእጄ ፡ ያድን ፡ ዘንድ ፡ የቻለ ፡ ማን ፡ ነው ፧

15 ፤ አኹንም ፡ ሕዝቅያስ ፡ አያስታችኹ ፥ እንዲህም ፡ አያባብላችኹ ፥ አትመኑትም ፤ ከአሕዛብና ፡ ከመንግሥታት ፡
አማልክት ፡ ኹሉ ፡ ሕዝቡን ፡ ከእጄና ፡ ከአባቶቼ ፡ እጅ ፡ ያድን ፡ ዘንድ ፡ ዘንድ ፡ ማንም ፡ አልቻለም ፤ ይልቁንስ ፡
አምላካችኹ ፡ ከእጄ ፡ ያድናችኹ ፡ ዘንድ ፡ እንዴት ፡ ይችላል ፧

16 ፤ ባሪያዎቹም ፡ ደግሞ ፡ በአምላክ ፡ በእግዚአብሔርና ፡ በባሪያው ፡ በሕዝቅያስ ፡ ላይ ፡ ሌላ ፡ ብዙ ፡ ነገር ፡ ተናገሩ ።

17 ፤ ደግሞም ፡ የእስራኤልን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለመስደብ ፥ በርሱም ፡ ላይ ፡ ለመናገር ። የምድር ፡ አሕዛብ ፡
አማልክት ፡ ሕዝባቸውን ፡ ከእጄ ፡ ያድኑ ፡ ዘንድ ፡ እንዳልቻሉ ፥ እንዲሁ ፡ የሕዝቅያስ ፡ አምላክ ፡ ሕዝቡን ፡ ከእጄ ፡

ያድን ፡ ዘንድ ፡ አይችልም ፡ የሚል ፡ ደብዳቤ ፡ ጻፈ ።

18 ፤ ከተማዪቱንም ፡ እንዲወስዱ ፥ በቅጥር ፡ ላይ ፡ የተቀመጡትን ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ሕዝብ ፡ ያስፈሩና ፡ ያስደነግጡ ፡ ዘንድ ፥ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ በዕብራይስጥ ፡ ቋንቋ ፡ ይጮኹባቸው ፡ ነበር ።

19 ፤ በሰውም ፡ እጅ ፡ በተሠሩ ፡ በምድር ፡ አሕዛብ ፡ አማልክት ፡ ላይ ፡ እንደሚናገሩ ፡ መጠን ፡ በኢየሩሳሌም ፡ አምላክ ፡ ላይ ፡ ተናገሩ ።

20 ፤ ንጉሡም ፡ ሕዝቅያስና ፡ የዓሞጽ ፡ ልጅ ፡ ነቢዩ ፡ ኢሳይያስ ፡ ስለዚህ ፡ ጸለዩ ፥ ወደ ፡ ሰማይም ፡ ጮኹ ።

21 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ጽኑዓን ፡ ኀያላኑንና ፡ መሳፍንቱን ፡ አለቃዎቹንም ፡ ከአሶር ፡ ንጉሥ ፡ ሰፈር ፡ እንዲያጠፉ ፡ መልአኩን ፡ ሰደደ ። የአሶርም ፡ ንጉሥ ፡ ዐፍሮ ፡ ወደ ፡ አገሩ ፡ ተመለሰ ። ወደአምላኩም ፡ ቤት ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ ከወገቡ ፡ የወጡት ፡ ልጆቹ ፡ በዚያ ፡ በሰይፍ ፡ ገደሉት ።

22 ፤ እንዲሁም ፡ እግዚአብሔር ፡ ሕዝቅያስንና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የሚኖሩትን ፡ ከአሶር ፡ ንጉሥ ፡ ከሰናክሬም ፡ እጅ ፡ ከኹሉም ፡ እጅ ፡ አዳናቸው ፤ በዙሪያቸውም ፡ ካለው ፡ ኹሉ ፡ አሳረፋቸው ።

23 ፤ ብዙዎቹም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መባ ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ይመጡ ፡ ነበር ፥ ለይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡ ለሕዝቅያስ ፡ እጅ ፡ መንሻ ፡ ይሰጡ ፡ ነበር ፤ ርሱም ፡ ከዚህ ፡ ነገር ፡ በኋላ ፡ በአሕዛብ ፡ ኹሉ ፡ ፊት ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለ ።

24 ፤ በዚያም ፡ ወራት ፡ ሕዝቅያስ ፡ እስኪሞት ፡ ድረስ ፡ ታመመ ፥ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ጸለየ ፤ ርሱም ፡ ተናገረው ፥ ምልክትም ፡ ሰጠው ።

25 ፤ ሕዝቅያስ ፡ ግን ፡ እንደተቀበለው ፡ ቸርነት ፡ መጠን ፡ አላደረገም ፥ ልቡም ፡ ኰራ ፤ ስለዚህም ፡ በርሱና ፡ በይሁዳ ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ ላይ ፡ ቍጣ ፡ ኾነ ።

26 ፤ ሕዝቅያስም ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ ስለልቡ ፡ ኵራት ፡ ሰውነቱን ፡ አዋረደ ፥ የእግዚአብሔርም ፡ ቍጣ ፡ በሕዝቅያስ ፡ ዘመን ፡ አልመጣባቸውም ።

27 ፤ ለሕዝቅያስም ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ሀብትና ፡ ክብር ፡ ነበረው ፤ ለብርና ፡ ለወርቅም ፥ ለከበረው ፡ ዕንቍና ፡ ለሽቱው ፥ ለጋሻውና ፡ ለከበረው ፡ ዕቃ ፡ ኹሉ ፡ ግምጃ ፡ ቤቶች ፡ ሠራ ።

28 ፤ ለእኽልና ፡ ለወይን ፡ ጠጅም ፡ ለዘይትም ፡ ዕቃ ፡ ቤቶች ፥ ለልዩ ፡ ልዩም ፡ እንስሳ ፡ ጋጥ ፥ ለመንጋዎችም ፡ በረት ፡ ሠራ ።

29 ፤ እግዚአብሔርም ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ጥሪት ፡ ሰጥቶት ፡ ነበርና ፥ ከተማዎችን ፡ ሠራ ፥ ብዙም ፡ የበግና ፡ የላም ፡ መንጋ ፡ ሰበሰበ ።

30 ፤ ይህም ፡ ሕዝቅያስ ፡ የላይኛውን ፡ የግዮንን ፡ ውሃ ፡ ምንጭ ፡ ደፈነ ፥ በዳዊትም ፡ ከተማ ፡ በምዕራብ ፡ በኩል ፡ አቅንቶ ፡ አወረደው ። የሕዝቅያስም ፡ ሥራ ፡ ኹሉ ፡ ተከናወነ ።

31 ፤ ነገር ፡ ግን ፥ የባቢሎን ፡ መሳፍንት ፡ መልእክተኛዎች ፡ በአገሩ ፡ ላይ ፡ ስለተደረገው ፡ ተኣምራት ፡ ይጠይቁት ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ርሱ ፡ በተላኩ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይፈትነውና ፡ በልቡ ፡ ያለውን ፡ ኹሉ ፡ ያውቅ ፡ ዘንድ ፡ ተወው ።

32 ፤ የሕዝቅያስም ፡ የቀረው ፡ ነገር ፥ ቸርነቱም ፥ እነሆ ፥ በዓሞጽ ፡ ልጅ ፡ በነቢዩ ፡ በኢሳይያስ ፡ ራእይ ፡ በይሁዳና ፡ በእስራኤልም ፡ ነገሥታት ፡ መጽሐፍ ፡ ተጽፏል ።

33 ፤ ሕዝቅያስም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋራ ፡ አንቀላፋ ፥ በዳዊትም ፡ ልጆች ፡ መቃብር ፡ በላይኛው ፡ ክፍል ፡ ቀበሩት ፤ በይሁዳና ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ የሚኖሩ ፡ ኹሉ ፡ በሞቱ ፡ አከበሩት ። ልጁም ፡ ምናሴ ፡ በርሱ ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ።

__________________መጽሐፈ ፡ ዜና ፡ መዋዕል ፡ ካልዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 33 ። __________________

ምዕራፍ ፡ 33 ።

1 ፤ ምናሴም ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የዐሥራ ፡ ኹለት ፡ ዓመት ፡ ልጅ ፡ ነበረ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ ዐምሳ ፡ ዐምስት ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ።

2 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ እንዳወጣቸው ፡ እንደ ፡ አሕዛብ ፡ ያለ ፡ ርኵሰት ፡ በእግዚአብሔር ፡

ፊት ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አደረገ ።

3 ፤ አባቱም ፡ ሕዝቅያስ ፡ ያፈረሳቸውን ፡ የኰረብታውን ፡ መስገጃዎች ፡ መልሶ ፡ ሠራ ፤ ለበዓሊምም ፡ መሠዊያ ፡ ሠራ ፥ የማምለኪያ ፡ ዐጸዶችንም ፡ ተከለ ፥ ለሰማይም ፡ ሰራዊት ፡ ኹሉ ፡ ሰገደ ፥ አመለካቸውም ።

4 ፤ እግዚአብሔርም ፦ ስሜ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ለዘለዓለም ፡ ይኖራል ፡ ባለው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ መሠዊያዎችን ፡ ሠራ ።

5 ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ በኹለቱ ፡ አደባባዮች ፡ ላይ ፡ ለሰማይ ፡ ሰራዊት ፡ ኹሉ ፡ መሠዊያዎችን ፡ ሠራ ።

6 ፤ በሄኖምም ፡ ልጅ ፡ ሸለቆ ፡ ውስጥ ፡ ልጆቹን ፡ በእሳት ፡ አሳለፈ ፤ ሞራ ፡ ገላጭም ፡ ኾነ ፥ አስማትም ፡ አደረገ ፥ መተተኛም ፡ ነበረ ፥ መናፍስት ፡ ጠሪዎችንና ፡ ጠንቋዮችንም ፡ ሰበሰበ ፤ ያስቈጣውም ፡ ዘንድ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እጅግ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አደረገ ።

7 ፤ 8 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ለዳዊትና ፡ ለልጁ ፡ ለሰሎሞን ፦ በዚህ ፡ ቤት ፡ ከእስራኤልም ፡ ነገድ ፡ ኹሉ ፡ በመረጥኋት ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ስሜን ፡ ለዘለዓለም ፡ አኖራለኹ ፤ ያዘዝኋቸውንም ፡ ኹሉ ፥ በሙሴ ፡ የተሰጠውን ፡ ሕግና ፡ ሥርዐት ፡ ፍርድንም ፡ ኹሉ ፡ ቢያደርጉ ፡ ቢጠብቁም ፥ ለአባቶቻቸኹ ፡ ከሰጠኋት ፡ ምድር ፡ የእስራኤልን ፡ እግር ፡ እንደ ፡ ገና ፡ አላርቅም ፡ ባለበት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ የሠራውን ፡ የጣዖት ፡ የተቀረጸውን ፡ ምስል ፡ አቆመ ።

9 ፤ ምናሴም ፡ እግዚአብሔር ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ ካጠፋቸው ፡ ከአሕዛብ ፡ ይልቅ ፡ ክፉ ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ በይሁዳና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የሚኖሩትን ፡ አሳተ ።

10 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ምናሴንና ፡ ሕዝቡን ፡ ተናገራቸው ፤ ግን ፡ አልሰሙትም ።

11 ፤ ስለዚህም ፡ እግዚአብሔር ፡ የአሶርን ፡ ንጉሥ ፡ ሰራዊት ፡ አለቃዎች ፡ አመጣባቸው ፤ ምናሴንም ፡ በዛንጅር ፡ ያዙት ፥ በሰንሰለትም ፡ አስረው ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ወሰዱት ።

12 ፤ በተጨነቀም ፡ ጊዜ ፡ አምላኩን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፈለገ ፥ በአባቶቹም ፡ አምላክ ፡ ፊት ፡ ሰውነቱን ፡ እጅግ ፡ አዋረደ ፥

13 ፤ ወደ ፡ ርሱም ፡ ጸለየ ፤ ርሱም ፡ ተለመነው ፥ ጸሎቱንም ፡ ሰማው ፥ ወደ ፡ መንግሥቱም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ መለሰው ፤ ምናሴም ፡ እግዚአብሔር ፡ ርሱ ፡ አምላክ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ ዐወቀ ።

14 ፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በዳዊት ፡ ከተማ ፡ በስተውጭው ፡ ከግዮን ፡ ምዕራብ ፡ በሸለቆው ፡ ውስጥ ፡ እስከዓሳ ፡ በር ፡ መግቢያ ፡ ድረስ ፡ ቅጥር ፡ ሠራ ። በዖፌልም ፡ አዞረበት ፥ እጅግም ፡ ከፍ ፡ አደረገው ፤ በተመሸጉትም ፡ በይሁዳ ፡ ከተማዎች ፡ ኹሉ ፡ የጭፍራ ፡ አለቃዎችን ፡ አኖረ ።

15 ፤ እንግዳዎችንም ፡ አማልክትና ፡ ጣዖቱንም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አራቀ ፥ የእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ ባለበት ፡ ተራራ ፡ ላይና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የሠራቸውን ፡ መሠዊያዎች ፡ ኹሉ ፡ ወስዶ ፡ ከከተማዪቱ ፡ በስተውጭ ፡ ጣላቸው ።

16 ፤ የእግዚአብሔርንም ፡ መሠዊያ ፡ ደግሞ ፡ ዐደሰ ፥ የደኅንነትና ፡ የምስጋናም ፡ መሥዋዕት ፡ ሠዋበት ፤ ይሁዳም ፡ የእስራኤልን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንዲያመልኩ ፡ አዘዘ ።

17 ፤ ሕዝቡ ፡ ግን ፡ ገና ፡ በኰረብታው ፡ መስገጃዎች ፡ ይሠዋ ፡ ነበር ፤ ቢኾንም ፡ ለአምላኩ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ብቻ ፡ ነበር ።

18 ፤ የምናሴም ፡ የቀረው ፡ ነገር ፥ ወደ ፡ አምላኩም ፡ የጸለየው ፡ ጸሎት ፥ በእስራኤልም ፡ አምላክ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ የነገሩት ፡ የነቢያት ፡ ቃል ፥ እንሆ ፥ በእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ መጽሐፍ ፡ ተጽፏል ።

19 ፤ ደግሞም ፡ ጸሎቱ ፥ እግዚአብሔርም ፡ እንደተለመነው ፥ ኀጢአቱና ፡ መተላለፉ ፡ ኹሉ ፥ ራሱንም ፡ ሳያዋርድ ፡ የኰረብታው ፡ መስገጃዎችን ፡ የሠራበት ፡ የማምለኪያ ፡ ዐጸዱንና ፡ የተቀረጹትንም ፡ ምስሎች ፡ የተከለበት ፡ ስፍራ ፥ እንሆ ፥ በባለራእዩ ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ ተጽፏል ።

20 ፤ ምናሴም ፡ ከአባቶቹ ፡ ጋራ ፡ አንቀላፋ ፥ በቤቱም ፡ ቀበሩት ፤ ልጁም ፡ ዓሞጽ ፡ በርሱ ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ።

21 ፤ ዓሞጽ ፡ መንገሥ ፡ በዠመረ ፡ ጊዜ ፡ የኻያ ፡ ኹለት ፡ ዓመት ፡ ጕልማሳ ፡ ነበረ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ ኹለት ፡ ዓመት ፡

ነገሠ ።

22 ፤ አባቱም ፡ ምናሴ ፡ እንዳደረገ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ አደረገ ፤ ዓሞጽም ፡ አባቱ ፡ ምናሴ ፡ ለሠራቸው ፡ ለተቀረጹት ፡ ምስሎች ፡ ኹሉ ፡ ሠዋ ፥ አመለካቸውም ።

23 ፤ አባቱም ፡ ምናሴ ፡ ሰውነቱን ፡ እንዳዋረደ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ አንዳላዋረደ ፡ በእግዚአብሔርም ፡ ሰውነቱን ፡ አላዋረደም ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ዓሞጽ ፡ መተላለፉን ፡ እጅግ ፡ አበዛ ።

24 ፤ ባሪያዎቹም ፡ ተማምለው ፡ በቤቱ ፡ ገደሉት ።

25 ፤ የአገሩ ፡ ሕዝብ ፡ ግን ፡ በንጉሡ ፡ በዓሞጽ ፡ ላይ ፡ የተማማሉትን ፡ ኹሉ ፡ ገደሉ ፤ የአገሩም ፡ ሕዝብ ፡ ልጁን ፡ ኢዮስያስን ፡ በርሱ ፡ ፋንታ ፡ አነገሡ ።

____________________መጽሐፈ ፡ ዜና ፡ መዋዕል ፡ ካልዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 34 ። ____________________

ምዕራፍ ፡ 34 ።

1 ፤ ኢዮስያስም ፡ መንገሥ ፡ በዠመረ ፡ ጊዜ ፡ የስምንት ፡ ዓመት ፡ ልጅ ፡ ነበረ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ ሠላሳ ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ።

2 ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ቅን ፡ ነገር ፡ አደረገ ፥ በአባቱም ፡ በዳዊት ፡ መንገድ ፡ ኼደ ፤ ወደ ፡ ቀኝም ፡ ወደ ፡ ግራም ፡ አላለም ።

3 ፤ በነገሠም ፡ በስምንተኛው ፡ ዓመት ፡ ገና ፡ ብላቴና ፡ ሳለ ፡ የአባቱን ፡ የዳዊትን ፡ አምላክ ፡ ይፈልግ ፡ ዠመር ፤ በዐሥራ ፡ ኹለተኛውም ፡ ዓመት ፡ ይሁዳንና ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ ከኰረብታው ፡ መስገጃዎችና ፡ ከማምለኪያ ፡ ዐጸዶቹ ፥ ከተቀረጹትና ፡ ቀልጠው ፡ ከተሠሩት ፡ ምስሎች ፡ ያነጻ ፡ ዠመር ።

4 ፤ የበዓሊምንም ፡ መሠዊያዎች ፡ በፊቱ ፡ አፈረሱ ፤ በላዩም ፡ የነበሩትን ፡ የፀሓዩን ፡ ምስሎች ፡ የማምለኪያ ፡ ዐጸዶቹንም ፡ ቈረጠ ፤ የተቀረጹትንና ፡ ቀልጠው ፡ የተሠሩትን ፡ ምስሎች ፡ ሰባበረ ፥ አደቀቃቸውም ፥ ይሠዉላቸው ፡ በነበሩት ፡ ሰዎች ፡ መቃብርም ፡ ላይ ፡ በተናቸው ።

5 ፤ የካህናታቸውንም ፡ ዐጥንት ፡ በመሠዊያቸው ፡ ላይ ፡ አቃጠለ ፤ ይሁዳንና ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ አንጻ ።

6 ፤ የምናሴንና ፡ የኤፍሬምንም ፡ የስምዖንና ፡ የንፍታሌምንም ፡ ከተማዎች ፥ በዙሪያቸውም ፡ ያለውን ፡ ቦታ ፡ እንዲሁ ፡ አነጻ ።

7 ፤ መሠዊያዎቹንም ፡ አፈረሰ ፥ የማምለኪያ ፡ ዐጸዶቹንና ፡ የተቀረጹትን ፡ ምስሎች ፡ አደቀቀ ፥ በእስራኤልም ፡ አገር ፡ ኹሉ ፡ የፀሓይን ፡ ምስሎች ፡ ኹሉ ፡ ቈራረጠ ፥ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ ተመለሰ ።

8 ፤ በነገሠም ፡ በዐሥራ ፡ ስምንተኛው ፡ ዓመት ፡ ምድሪቱንና ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ካነጻ ፡ በ፟ኋላ ፥ የኤዜልያስ ፡ ልጅ ፡ ሳፋን ፥ የከተማዪቱም ፡ አለቃ ፡ መዕሴያ ፥ ታሪክ ፡ ጸሓፊም ፡ የኢዮአካዝ ፡ ልጅ ፡ ኢዮአክ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ የአምላኩን ፡ ቤት ፡ ይጠግኑ ፡ ዘንድ ፡ ሰደዳቸው ።

9 ፤ ወደ ፡ ታላቁም ፡ ካህን ፡ ወደ ፡ ኬልቅያስ ፡ መጡ ፤ ሌዋውያኑም ፡ በረኞች ፡ ከምናሴና ፡ ከኤፍሬም ፡ ከቀረውም ፡ ከእስራኤል ፡ ኹሉ ፥ ከይሁዳና ፡ ከብንያም ፡ ኹሉ ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ ከሚኖሩት ፡ የሰበሰቡትን ፥ ወደእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ የቀረበውን ፡ ገንዘብ ፡ ሰጡት ።

10 ፤ የእግዚአብሔርንም ፡ ቤት ፡ በሚሠሩት ፡ ላይ ፡ ለተሾሙት ፡ ሰጡ ፤ እነርሱም ፡ ይጠግኑና ፡ ያድሱ ፡ ዘንድ ፥ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ለሚሠሩ ፡ ሠራተኞች ፡ ሰጡ ።

11 ፤ የይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ ላፈረሱት ፡ ቤት ፡ ሠረገላዎች ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፥ ለማጋጠሚያም ፡ ዕንጨት ፡ የተጠረበውንም ፡ ድንጋይ ፡ ይገዙ ፡ ዘንድ ፡ ለዐናጢዎችና ፡ ለጠራቢዎች ፡ ሰጡ ።

12 ፤ ሰዎቹም ፡ ሥራውን ፡ በመታመን ፡ አደረጉ ፤ በእነርሱም ፡ ላይ ፡ የተሾሙት ፥ ሥራውንም ፡ የሚያሠሩት ፡ ሌዋውያን ፡ ከሜራሪ ፡ ልጆች ፡ ኢኤትና ፡ ዐብድዩ ፥ ከቀአትም ፡ ልጆች ፡ ዘካርያስና ፡ ሜሱላም ፡ ነበሩ ። ከሌዋውያንም ፡ ወገን ፡ በዜማ ፡ ዕቃ ፡ ዐዋቂዎች ፡ የነበሩ ፡ ኹሉ ፡

13 ፤ በተሸካሚዎችና ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ሥራ ፡ በሚሠሩ ፡ ላይ ፡ ተሾመው ፡ ነበር ፤ ጸሓፊዎቹና ፡ አለቃዎቹም ፡ በረኛዎቹም ፡ ከሌዋውያን ፡ ወገን ፡ ነበሩ ።

14 ፤ ወደእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ የቀረበውን ፡ ገንዘብ ፡ ባመጡ ፡ ጊዜ ፡ ካህኑ ፡ ኬልቅያስም ፡ በሙሴ ፡ እጅ ፡ የተሰጠውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ መጽሐፍ ፡ አገኘ ።

15 ፤ ኬልቅያስም ፡ ጸሓፊውን ፡ ሳፋንን ፦ የሕጉን ፡ መጽሐፍ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አግኝቻለኹ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ። ኬልቅያስም ፡ መጽሐፉን ፡ ለሳፋን ፡ ሰጠው ።

16 ፤ ሳፋንም ፡ መጽሐፉን ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ አመጣ ፤ ለንጉሡም ። ባሪያዎችኽ ፡ የተሰጣቸውን ፡ ትእዛዝ ፡ ኹሉ ፡ ያደርጋሉ ፤

17 ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ የተገኘውን ፡ ገንዘብ ፡ አፈሰሱ ፥ በሥራውም ፡ ላይ ፡ ለተሾሙትና ፡ ለሠራተኛዎቹ ፡ ሰጡ ፡ ብሎ ፡ አወራለት ።

18 ፤ ጸሓፊውም ፡ ሳፋን ፡ ለንጉሡ ፦ ካህኑ ፡ ኬልቅያስ ፡ መጽሐፍ ፡ ሰጠኝ ፡ ብሎ ፡ ነገረው ። ሳፋንም ፡ በንጉሡ ፡ ፊት ፡ አነበበው ።

19 ፤ ንጉሡም ፡ የሕጉን ፡ ቃል ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ልብሱን ፡ ቀደደ ።

20 ፤ ንጉሡም ፡ ኬልቅያስን ፥ የሳፋንንም ፡ ልጅ ፡ አኪቃምን ፥ የሚክያስንም ፡ ልጅ ፡ ዐብዶንን ፥ ጸሓፊውንም ፡ ሳፋንን ፥ የንጉሡንም ፡ ብላቴና ፡ ዐሳያን ፦

21 ፤ በዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈውን ፡ ኹሉ ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ አባቶቻችን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስላልጠበቁ ፥ በላያችን ፡ የነደደ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ እጅግ ፡ ነውና ፥ ኼዳችኹ ፡ ስለተገኘው ፡ የመጽሐፍ ፡ ቃል ፡ ለእኔ ፡ በእስራኤልና ፡ በይሁዳም ፡ ለቀሩት ፡ እግዚአብሔርን ፡ ጠይቁ ፡ ብሎ ፡ አዘዛቸው ።

22 ፤ ኬልቅያስና ፡ እነዚያ ፡ ንጉሥ ፡ ያዘዛቸው ፡ ወደልብስ ፡ ጠባቂው ፡ ወደሐስራ ፡ ልጅ ፡ ወደቲቁዋ ፡ ልጅ ፡ ወደሴሌም ፡ ሚስት ፡ ወደ ፡ ነቢዪቱ ፡ ወደ ፡ ሕልዳና ፡ ኼዱ ፤ ርሷም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ በከተማዪቱ ፡ በኹለተኛው ፡ ክፍል ፡ ተቀምጣ ፡ ነበር ፤ ይህንም ፡ ነገር ፡ ነገሯት ።

23 ፤ ርሷም ፡ አለቻቸው ፦ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ወደ ፡ እኔ ፡ ለላካችኹ ፡ ሰው ፡ እንዲህ ፡ ብላችኹ ፡ ንገሩት ፦

24 ፤ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ እንሆ ፥ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ፊት ፡ በተነበበው ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፉትን ፡ ቃላት ፡ ኹሉ ፥ ማለት ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፥ በዚህ ፡ ስፍራና ፡ በሚኖሩበት ፡ ላይ ፡ አመጣለኹ ።

25 ፤ በእጃቸው ፡ ሥራ ፡ ኹሉ ፡ ሊያስቈጡኝ ፡ ትተውኛልና ፥ ለሌላዎችም ፡ አማልክት ፡ ዐጥነዋልና ፥ ቍጣዬ ፡ በዚህ ፡ ስፍራ ፡ ይነዻል ፥ አይጠፋምም ።

26 ፤ እግዚአብሔርን ፡ ለመጠየቅ ፡ ለላካችኹ ፡ ለይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ እንዲህ ፡ በሉት ፦ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ስለሰማኸው ፡ ቃል ፡ ልብኽ ፡ ገር ፡ ኾኗልና ፥

27 ፤ በፊቴም ፡ ራስኽን ፡ አዋርደኻልና ፥ በዚህም ፡ ስፍራና ፡ በሚኖሩበት ፡ ላይ ፡ ቃሌን ፡ በሰማኽ ፡ ጊዜ ፡ ራስኽን ፡ አዋርደኻልና ፥ ልብስኽንም ፡ ቀዷኽ ፡ በፊቴ ፡ አልቅሰኻልና ፥ እኔ ፡ ደግሞ ፡ ሰምቻለኹ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

28 ፤ እንሆ ፥ ወደ ፡ አባቶችኽ ፡ እሰበስብኻለኹ ፥ በሰላምም ፡ ወደ ፡ መቃብርኽ ፡ ትሰበሰባለኽ ፤ በዚህም ፡ ስፍራና ፡ በሚኖሩበት ፡ ላይ ፡ የማመጣውን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ኹሉ ፡ ዐይኖችኽ ፡ አያዩም ። ይህንም ፡ ለንጉሥ ፡ አወሩለት ።

29 ፤ ንጉሡም ፡ ላከ ፥ የይሁዳንና ፡ የኢየሩሳሌምንም ፡ ሽማግሌዎች ፡ ኹሉ ፡ ሰበሰበ ።

30 ፤ ንጉሡም ፡ የይሁዳም ፡ ሰዎች ፡ ኹሉ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ የሚኖሩና ፡ ካህናቱ ፥ ሌዋውያኑም ፥ ሕዝቡም ፡ ኹሉ ፡ ከታናሹ ፡ ዠምሮ ፡ እስከ ፡ ታላቁ ፡ ድረስ ፡ ወደእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ወጡ ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ የተገኘውን ፡ የቃል ፡ ኪዳኑን ፡ መጽሐፍ ፡ ቃል ፡ ኹሉ ፡ በዦሯቸው ፡ አነበበ ።

31 ፤ ንጉሡም ፡ በስፍራው ፡ ቆሞ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ተከትሎ ፡ እንዲኼድ ፥ ትእዛዙንና ፡ ምስክሩን ፡ ሥርዐቱንም ፡

በፍጹም ፡ ልቡና ፡ በፍጹም ፡ ነፍሱ ፡ እንዲጠብቅ ፥ በዚህም ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈውን ፡ የቃል ፡ ኪዳን ፡ ቃል ፡ እንዲያደርግ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አደረገ ።

32 ፤ በኢየሩሳሌምና ፡ በብንያምም ፡ የተገኙትን ፡ ኹሉ ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ አማለ ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ የሚኖሩት ፡ የአባቶቻቸው ፡ አምላክ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ እንዳዘዘ ፡ አደረጉ ።

33 ፤ ኢዮስያስም ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ምድር ፡ ኹሉ ፡ ርኩሱን ፡ ኹሉ ፡ አስወገደ ፥ በእስራኤልም ፡ የተገኙትን ፡ ኹሉ ፡ አምላካቸውን ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንዲያመልኩ ፡ አደረገ ። በዘመኑ ፡ ኹሉ ፡ የአባቶቻቸውን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ከመከተል ፡ አልራቁም ።

__________________መጽሐፈ ፡ ዜና ፡ መዋዕል ፡ ካልዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 35 ። __________________

ምዕራፍ ፡ 35 ።

1 ፤ ኢዮስያስም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ፋሲካ ፡ አደረገ ፤ በመዠመሪያውም ፡ ወር ፡ በዐሥራ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ ፋሲካውን ፡ ዐረዱ ።

2 ፤ ካህናቱንም ፡ በየሥርዐታቸውም ፡ አቆመ ፥ በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ ያገለግሉ ፡ ዘንድ ፡ አጸናቸው ።

3 ፤ እስራኤልንም ፡ ኹሉ ፡ ያስተምሩ ፡ ለነበሩት ፥ ለእግዚአብሔርም ፡ ለተቀደሱት ፡ ሌዋውያን ፡ እንዲህ ፡ አለ ። ቅዱሱን ፡ ታቦት ፡ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ የዳዊት ፡ ልጅ ፡ ሰሎሞን ፡ በሠራው ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ አኑሩት ፤ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በትከሻችኹ ፡ ላይ ፡ ሸክም ፡ አይኾንባችኹም ፤ አኹንም ፡ አምላካችኹን ፡ እግዚአብሔርንና ፡ ሕዝቡን ፡ እስራኤልን ፡ አገልግሉ ፤

4 ፤ የእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ እንደ ፡ ጻፈው ፡ ልጁም ፡ ሰሎሞን ፡ እንደ ፡ ጻፈው ፡ በየሰሞናችኹና ፡ በያባቶቻችኹ ፡ ቤቶች ፡ ተዘጋጁ ፤

5 ፤ እንደ ፡ ሕዝቡም ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ ወንድሞቻችኹ ፡ በያባቶች ፡ ቤቶች ፡ ኾናችኹ ፡ በመቅደሱ ፡
ቁሙ ፤ የሌዋውያንም ፡ ነገድ ፡ በየወገናቸው ፡ እንደ ፡ ተከፈሉ ፡ እናንተ ፡ ተከፈሉ ፤ ፋሲካውንም ፡ ዕረዱ ፥

6 ፤ እናንተም ፡ ተቀደሱ ፥ እግዚአብሔርም ፡ በሙሴ ፡ እጅ ፡ የተናገረውን ፡ ቃል ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ለወንድሞቻችኹ ፡ አዘጋጁ ።

7 ፤ ኢዮስያስም ፡ ለፋሲካው ፡ መሥዋዕት ፡ እንዲኾን ፡ በዚያ ፡ ለነበሩት ፡ ለሕዝቡ ፡ ልጆች ፡ ከመንጋው ፡ ሠላሳ ፡ ሺሕ ፡ የበግና ፡ የፍየል ፡ ጠቦቶች ፥ ሦስት ፡ ሺሕም ፡ ወይፈኖች ፡ ሰጣቸው ፤ እነዚህም ፡ ከንጉሡ ፡ ሀብት ፡ ነበሩ ።

8 ፤ መሳፍንቱም ፡ ለሕዝቡና ፡ ለካህናቱ ፡ ለሌዋውያኑም ፡ በፈቃዳቸው ፡ ሰጡ ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ አለቃዎች ፥ ኬልቅያስ ፥ ዘካርያስ ፥ ይሒኤል ፥ ለፋሲካው ፡ መሥዋዕት ፡ እንዲኾን ፡ ኹለት ፡ ሺሕ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ በጎችና ፡ ፍየሎች ፥ ሦስት ፡ መቶም ፡ በሬዎች ፡ ለካህናቱ ፡ ሰጡ ።

9 ፤ የሌዋውያኑም ፡ አለቃዎች ፡ ኮናንያ ፥ ወንድሞቹም ፡ ሸማያና ፡ ናትናኤል ፥ ሐሸቢያ ፥ ይዒኤል ፥ ዮዛባት ፡ ለፋሲካው ፡ መሥዋዕት ፡ እንዲኾን ፡ ዐምስት ፡ ሺሕ ፡ በጎችና ፡ ፍየሎች ፥ ዐምስት ፡ መቶም ፡ በሬዎች ፡ ለሌዋውያን ፡ ሰጡ ።

10 ፤ አገልግሎቱም ፡ ተዘጋጀ ፥ ካህናቱም ፡ በስፍራቸው ፥ ሌዋውያኑም ፡ በየክፍላቸው ፡ እንደ ፡ ንጉሥ ፡ ትእዛዝ ፡ ቆሙ ።

11 ፤ ፋሲካውንም ፡ ዐረዱ ፥ ሌዋውያኑም ፡ ቍርበቱን ፡ ገፈፉ ፥ ካህናቱም ፡ ከእጃቸው ፡ የተቀበሉትን ፡ ደም ፡ ረጩ ።

12 ፤ በሙሴም ፡ መጽሐፍ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ያቀርቡ ፡ ዘንድ ፡ በያባቶቻቸው ፡ ቤቶች ፡ ለሕዝቡ ፡ ልጆች ፡ እንዲሰጡ ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፡ ለዩ ። እንዲሁም ፡ በበሬዎቹ ፡ አደረጉ ።

13 ፤ ፋሲካውንም ፡ እንደ ፡ ሥርዐቱ ፡ በእሳት ፡ ጠበሱ ፤ የተቀደሰውንም ፡ ቍርባን ፡ በምንቸትና ፡ በሰታቴ ፡ በድስትም ፡ ቀቀሉ ፥ ለሕዝቡም ፡ ልጆች ፡ ኹሉ ፡ በፍጥነት ፡ አደረሱ ።

14 ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ለራሳቸውና ፡ ለካህናቱ ፡ አዘጋጁ ፤ የአሮንም ፡ ልጆች ፡ ካህናቱ ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕትና ፡ ስቡን ፡ ለማቅረብ ፡ እስከ ፡ ሌሊት ፡ ድረስ ፡ ይሠሩ ፡ ነበርና ፥ ስለዚህ ፡ ሌዋውያን ፡ ለራሳቸውና ፡ ለአሮን ፡ ልጆች ፡

ለካህናቱ ፡ አዘጋጁ ።

15 ፤ የአሣፍም ፡ ልጆች ፡ መዘምራን ፡ እንደ ፡ ዳዊት ፥ እንደ ፡ አሣፍም ፡ እንደ ፡ ኤማንም ፡ የንጉሡም ፡ ባለራእይ ፡ እንደ ፡ ነበረው ፡ እንደ ፡ ኤዶታም ፡ ትእዛዝ ፡ በየስፍራቸው ፡ ነበሩ ፤ በረኞቹም ፡ በሮቹን ፡ ኹሉ ፡ ይጠብቁ ፡ ነበር ፤ ወንድሞቻቸውም ፡ ሌዋውያን ፡ ያዘጋጁላቸው ፡ ነበርና ፥ ከአገልግሎታቸው ፡ ይርቁ ፡ ዘንድ ፡ አያስፈልጋቸውም ፡ ነበር ።

16 ፤ እንደ ፡ ንጉሡም ፡ እንደ ፡ ኢዮስያስ ፡ ትእዛዝ ፡ በእግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፡ ያቀርቡ ፡ ዘንድ ፥ ፋሲካውንም ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ የእግዚአብሔር ፡ አገልግሎት ፡ ኹሉ ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ተዘጋጀ ።

17 ፤ የተገኙትም ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ፋሲካውን ፥ ሰባት ፡ ቀንም ፡ የቂጣ ፡ በዓልን ፡ አደረጉ ።

18 ፤ ከነቢዩ ፡ ከሳሙኤል ፡ ዘመን ፡ ዠምሮ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ፋሲካ ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ከቶ ፡ አልተደረገም ፤ ከእስራኤልም ፡ ነገሥታት ፡ ኹሉ ፡ ኢዮስያስና ፡ ካህናቱ ፥ ሌዋውያኑም ፥ በዚያም ፡ የተገኙ ፡ የይሁዳና ፡ የእስራኤል ፡ ሰዎች ፡ ኹሉ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ የሚኖሩት ፡ እንዳደረጉት ፡ ያለ ፡ ፋሲካ ፡ ያደረገ ፡ የለም ።

19 ፤ ይህም ፡ ፋሲካ ፡ ኢዮስያስ ፡ በነገሠ ፡ በዐሥራ ፡ ስምንተኛው ፡ ዓመት ፡ ተደረገ ።

20 ፤ ከዚህም ፡ ኹሉ ፡ በኋላ ፥ ኢዮስያስም ፡ ቤቱ ፡ መቅደሱን ፡ ካሰናዳ ፡ በኋላ ፥ የግብጽ ፡ ንጉሥ ፡ ኒካዑ ፡ በኤፍራጥስ ፡ ወንዝ ፡ አጠገብ ፡ ባለው ፡ በከርከሚሽ ፡ ላይ ፡ ይዋጋ ፡ ዘንድ ፡ ወጣ ፤ ኢዮስያስም ፡ ሊጋጠመው ፡ ወጣ ።

21 ፤ ርሱም ፦ የይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ፥ ከአንተ ፡ ጋራ ፡ ምን ፡ አለኝ ፧ በምዋጋበት ፡ በሌላ ፡ ቤት ፡ ላይ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ባንተ ፡ ላይ ፡ ዛሬ ፡ አልመጣኹም ፤ እግዚአብሔርም ፡ እንድቸኵል ፡ አዞኛል ፤ ከእኔ ፡ ጋራ ፡ ያለው ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳያጠፋኽ ፡ ይህን ፡ በርሱ ፡ ላይ ፡ ከማድረግ ፡ ተመለስ ፡ ብሎ ፡ መልእክተኛዎችን ፡ ላከበት ።

22 ፤ ኢዮስያስ ፡ ግን ፡ ይዋጋው ፡ ዘንድ ፡ ተጸናና ፡ እንጂ ፡ ፊቱን ፡ ከርሱ ፡ አልመለሰም ፤ በእግዚአብሔርም ፡ አፍ ፡ የተነገረውን ፡ የኒካዑን ፡ ቃል ፡ አልሰማም ፥ በመጊዶም ፡ ሸለቆ ፡ ይዋጋ ፡ ዘንድ ፡ መጣ ።

23 ፤ ቀስተኛዎችም ፡ ንጉሡን ፡ ኢዮስያስን ፡ ወጉት ፤ ንጉሡም ፡ ብላቴናዎቹን ፦ አጥብቄ ፡ ቈስያለኹና ፡ ከሰልፉ ፡ ውስጥ ፡ አውጡኝ ፡ አላቸው ።

24 ፤ ብላቴናዎቹም ፡ ከሠረገላው ፡ አውርደው ፡ ለርሱ ፡ በነበረው ፡ በኹለተኛው ፡ ሠረገላ ፡ ውስጥ ፡ አስቀመጡት ፥ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ አመጡት ፤ ርሱም ፡ ሞተ ፥ በአባቶቹም ፡ መቃብር ፡ ተቀበረ ፤ ይሁዳና ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ ኹሉ ፡ ለኢዮስያስ ፡ አለቀሱ ።

25 ፤ ኤርምያስም ፡ ለኢዮስያስ ፡ የልቅሶ ፡ ግጥም ፡ ገጠመለት ፤ እስከ ፡ ዛሬም ፡ ድረስ ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ መዘምራን ፡ ኹሉ ፡ በልቅሶ ፡ ግጥማቸው ፡ ስለ ፡ ኢዮስያስ ፡ ይናገሩ ፡ ነበር ፤ ይህም ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ወግ ፡ ኾኖ ፡ በልቅሶ ፡ ግጥም ፡ ተጽፏል ።

26 ፤ የቀረውም ፡ የኢዮስያስ ፡ ነገር ፥ በእግዚአብሔርም ፡ ሕግ ፡ አንደ ፡ ተጻፈ ፡ ያደረገው ፡ ቸርነት ፥

27 ፤ የፊተኛውና ፡ የኋለኛውም ፡ ነገሩ ፥ እንሆ ፥ በእስራኤልና ፡ በይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ መጽሐፍ ፡ ተጽፏል ።

## መጽሐፈ ፡ ዜና ፡ መዋዕል ፡ ካልዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 36 ።

ምዕራፍ ፡ 36 ።

1 ፤ የአገሩም ፡ ሰዎች ፡ የኢዮስያስን ፡ ልጅ ፡ ኢዮአክስን ፡ ወስደው ፡ በአባቱ ፡ ፋንታ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ አነገሡት ።

2 ፤ ኢዮአክስም ፡ መንገሥ ፡ በዠመረ ፡ ጊዜ ፡ የኻያ ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ጕልማሳ ፡ ነበረ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ ሦስት ፡ ወር ፡ ነገሠ ።

3 ፤ የግብጽም ፡ ንጉሥ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ከመንግሥቱ ፡ አወጣው ፥ መቶም ፡ መክሊት ፡ ብርና ፡ አንድ ፡ መክሊት ፡ ወርቅ ፡ ዕዳ ፡ ጣለበት ።

4 ፤ የግብጽም ፡ ንጉሥ ፡ ወንድሙን ፡ ኤልያቄምን ፡ በይሁዳና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ላይ ፡ አነገሠ ፥ ስሙንም ፡ ኢዮአቄም ፡ ብሎ ፡ ለወጠ ፤ ኒካዑም ፡ ወንድሙን ፡ ኢዮአክስን ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ ወሰደው ።

5 ፤ ኢዮአቄምም ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የኻያ ፡ ዐምስት ፡ ዓመት ፡ ጕልማሳ ፡ ነበረ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ ዐሥራ ፡
አንድ ፡ ዓመት ፡ ነገሠ ፤ በአምላኩም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ አደረገ ።

6 ፤ የባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነጾር ፡ በርሱ ፡ ላይ ፡ መጥቶ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ይወስደው ፡ ዘንድ ፡ በሰንሰለት ፡
አሰረው ።

7 ፤ ናቡከደነጾርም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ዕቃ ፡ ዐያሌውን ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ አፈለሰ ፥ በባቢሎንም ፡ በመቅደሱ ፡
ውስጥ ፡ አኖረው ።

8 ፤ የቀረውም ፡ የኢዮአቄም ፡ ነገር ፥ ያደረገውም ፡ ርኵሰት ፥ በርሱም ፡ የተገኘው ፡ ኹሉ ፥ እንሆ ፥ በእስራኤልና ፡
በይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ መጽሐፍ ፡ ተጽፏል ፤ ልጁም ፡ ዮአኪን ፡ በርሱ ፡ ፋንታ ፡ ነገሠ ።

9 ፤ ዮአኪንም ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የዐሥራ ፡ ስምንት ፡ ዓመት ፡ ጕልማሳ ፡ ነበረ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ ሦስት ፡
ወርና ፡ ዐሥር ፡ ቀን ፡ ነገሠ ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ አደረገ ።

10 ፤ ዓመቱ ፡ ባለፈ ፡ ጊዜ ፡ ንጉሡ ፡ ናቡከደነጾር ፡ ልኮ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ወሰደው ፥ የከበረውንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ቤት ፡ ዕቃ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ አስወሰደ ፤ ወንድሙንም ፡ ሴዴቅያስን ፡ በይሁዳና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ላይ ፡ አነገሠ ።

11 ፤ ሴዴቅያስ ፡ መንገሥ ፡ በጀመረ ፡ ጊዜ ፡ የኻያ ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ ጕልማሳ ፡ ነበረ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ ዐሥራ ፡ አንድ ፡
ዓመት ፡ ነገሠ ።

12 ፤ በአምላኩም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ አደረገ ፤ በእግዚአብሔርም ፡ አፍ ፡ በተናገረው ፡ በነቢዩ ፡ በኤርምያስ ፡
ፊት ፡ ራሱን ፡ አላዋረደም ።

13 ፤ ደግሞም ፡ በእግዚአብሔር ፡ አምሎት ፡ በነበረው ፡ በንጉሡ ፡ በናቡከደነጾር ፡ ላይ ፡ ዐመፀ ፤ ወደእስራኤልም ፡
አምላክ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳይመለስ ፡ ዐንገቱን ፡ አደነደነ ፡ ልቡንም ፡ አጠነከረ ።

14 ፤ ደግሞም ፡ የካህናቱ ፡ አለቃዎች ፡ ኹሉ ፡ ሕዝቡም ፡ እንደ ፡ አሕዛብ ፡ ያለ ፡ ርኵሰት ፡ ኹሉ ፡ መተላለፍን ፡
አበዙ ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ የቀደሰውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ አረከሱ ።

15 ፤ የአባቶቻቸውም ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሕዝቡና ፡ ለማደሪያው ፡ ስላዘነ ፡ ማለዳ ፡ ተነሥቶ ፡ በመልእክተኛዎቹ ፡
እጅ ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ይልክ ፡ ነበር ።

16 ፤ እነርሱ ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ እስኪወጣ ፡ ድረስ ፥ ፈውስም ፡ እስከማይገኝላቸው ፡
ድረስ ፥ በእግዚአብሔር ፡ መልእክተኛዎች ፡ ይሣለቁ ፥ ቃሉንም ፡ ያቃልሉ ፥ በነቢያቱም ፡ ላይ ፡ ያፌዙ ፡ ነበር ።

17 ፤ ስለዚህም ፡ የከለዳውያንን ፡ ንጉሥ ፡ አመጣባቸው ፤ ርሱም ፡ ጕልማሳዎቻቸውን ፡ በቤተ ፡ መቅደሱ ፡ ውስጥ ፡
በሰይፍ ፡ ገደላቸው ፤ ጕልማሳውንና ፡ ቈንጆዪቱን ፡ ሽማግሌውንና ፡ አሮጊውን ፡ አልማረም ፤ ኹሉንም ፡ በእጁ ፡
አሳልፎ ፡ ሰጠው ።

18 ፤ የእግዚአብሔርንም ፡ ቤት ፡ ዕቃ ፡ ኹሉ ፡ ታላቁንና ፡ ታናሹን ፥ የእግዚአብሔርንም ፡ ቤት ፡ መዝገብ ፥ የንጉሡንና ፡
የአለቃዎቹን ፡ መዝገብ ፥ እነዚህን ፡ ኹሉ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ወሰደ ።

19 ፤ የእግዚአብሔርንም ፡ ቤት ፡ አቃጠሉ ፥ የኢየሩሳሌምንም ፡ ቅጥር ፡ አፈረሱ ፥ አዳራሾቿንም ፡ በእሳት ፡
አቃጠሉ ፥ መልካሙንም ፡ ዕቃዋን ፡ ኹሉ ፡ አጠፉ ።

20 ፤ ከሰይፍም ፡ ያመለጡትን ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ማረካቸው ፤ የፋርስ ፡ ንጉሥም ፡ እስኪነግሥ ፡ ድረስ ፡ ለንጉሡና ፡
ለልጆቹ ፡ ባሪያዎች ፡ ኾኑ ፤

21 ፤ በኤርምያስም ፡ አፍ ፡ የተነገረው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ እንዲፈጸም ፥ ምድሪቱ ፡ ሰንበትን ፡ በማድረግ ፡
እስክታርፍ ፡ ድረስ ፤ በተፈታችበትም ፡ ዘመን ፡ ኹሉ ፥ ሰባ ፡ ዓመት ፡ እስኪፈጸም ፡ ድረስ ፥ ሰንበትን ፡ አገኘች ።

22 ፤ በኤርምያስም ፡ አፍ ፡ የተነገረው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ይፈጸም ፡ ዘንድ ፡ በፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ በቂሮስ ፡
በመጀመሪያው ፡ ዓመት ፡ እግዚአብሔር ፡ የፋርስን ፡ ንጉሥ ፡ የቂሮስን ፡ መንፈስ ፡ አስነሣ ፤ ርሱም ፦ የፋርስ ፡ ንጉሥ ፡
ቂሮስ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦

23 ፤ የሰማይ ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ የምድርን ፡ መንግሥታት ፡ ኹሉ ፡ ሰጥቶኛል ፤ በይሁዳም ፡ ባለችው ፡
በኢየሩሳሌም ፡ ቤት ፡ እሠራለት ፡ ዘንድ ፡ አዞኛል ፤ ከሕዝቡ ፡ ኹሉ ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ማንም ፡ ቢኾን ፡ አምላኩ ፡
እግዚአብሔር ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ይኹን ፥ ርሱም ፡ ይውጣ ፡ ብሎ ፡ በመንግሥቱ ፡ ኹሉ ፡ ዐዋጅ ፡ አስነገረ ፥ ደግሞም ፡
በጽሕፈት ፡ አደረገው ፨

# መጽሐፈ ፡ ዕዝራ ።

(ክለሳ.1.20020507)

## መጽሐፈ ፡ ዕዝራ ፥ ምዕራፍ ፡ 1 ።

ምዕራፍ ፡ 1 ።

1 ፤ በኤርምያስም ፡ አፍ ፡ የተናገረው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ይፈጸም ፡ ዘንድ ፡ በፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ በቂሮስ ፡ በመጀመሪያው ፡ ዓመት ፡ እግዚአብሔር ፡ የፋርስን ፡ ንጉሥ ፡ የቂሮስን ፡ መንፈስ ፡ አስነሣ ፤ ርሱም ፡ በመንግሥቱ ፡ ኹሉ ፡ ዐዋጅ ፡ አስነገረ ፥ ደግሞም ፡ በጽሕፈት ፡ አድርጎ ፡ እንዲህ ፡ አለ ።

2 ፤ የፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ ቂሮስ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ የሰማይ ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ የምድርን ፡ መንግሥታት ፡ ኹሉ ፡ ሰጥቶኛል ፤ በይሁዳም ፡ ባለችው ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ቤት ፡ እሠራለት ፡ ዘንድ ፡ አዞኛል ፤

3 ፤ ከሕዝቡ ፡ ኹሉ ፡ በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ማንም ፡ ቢኾን ፡ አምላኩ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ይኹን ፥ ርሱም ፡ በይሁዳ ፡ ወዳለችው ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ይውጣ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ ለሚኖረው ፡ አምላክ ፥ ለእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ይሥራ ፤

4 ፤ በሚኖርበትም ፡ ስፍራ ፡ ኹሉ ፡ ለቀረው ፡ ሰው ፡ የአገሩ ፡ ሰዎች ፡ በብርና ፡ በወርቅ ፡ በዕቃም ፡ በእንስሳም ፡ ይርዱት ፤ ይህም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ላለው ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ በፈቃዳቸው ፡ ከሚያቀርቡት ፡ ሌላ ፡ ይኹን ።

5 ፤ የይሁዳና ፡ የብንያም ፡ የአባቶች ፡ ቤቶች ፡ አለቃዎችም ፥ ካህናቱም ፥ ሌዋውያኑም ፥ በኢየሩሳሌም ፡ ያለውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ለመሥራት ፡ ይወጡ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ መንፈሳቸውን ፡ ያነሣሣው ፡ ኹሉ ፡ ተነሡ ።

6 ፤ በዙሪያቸውም ፡ ያሉ ፡ ኹሉ ፡ በፈቃዳቸው ፡ ካቀረቡት ፡ ኹሉ ፡ ሌላ ፡ በብር ፡ ዕቃና ፡ በወርቅ ፡ በገንዘቦችና ፡ በእንስሳዎች ፡ በሌላም ፡ ስጦታ ፡ አገዟቸው ።

7 ፤ ንጉሡ ፡ ቂሮስም ፡ ናቡከደነፆር ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ወስዶ ፡ በአማልክቱ ፡ ቤት ፡ ያኖራቸውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ዕቃዎች ፡ አወጣ ።

8 ፤ የፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ ቂሮስም ፡ በመዝገቡ ፡ ላይ ፡ በነበረው ፡ በሚትሪዳጡ ፡ እጅ ፡ አወጣቸው ፥ ለይሁዳም ፡ መስፍን ፡ ለሰሳብሳር ፡ ቈጠራቸው ።

9 ፤ ቍጥራቸውም ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ሠላሳ ፡ የወርቅ ፡ አንድ ፡ ሺሕም ፡ የብር ፡ ሣሕኖች ፥ ኻያ ፡ ዘጠኝም ፡ ቢላዎች ፥

10 ፤ ሠላሳ ፡ የወርቅ ፡ ደካዎች ፥ አራት ፡ መቶ ፡ ዐሥርም ፡ ሌላ ፡ ዐይነት ፡ የብር ፡ ደካዎች ፥ አንድ ፡ ሺሕም ፡ ሌላ ፡ ዕቃ ፡ ነበረ ።

11 ፤ የወርቁና ፡ የብሩ ፡ ዕቃዎች ፡ ኹሉ ፡ ዐምስት ፡ ሺሕ ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ነበሩ ፤ እነዚህንም ፡ ኹሉ ፡ ሰሳብሳር ፡ ከባቢሎን ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ከተመለሱ ፡ ምርኮኛዎቹ ፡ ጋራ ፡ ወሰደ ።

## መጽሐፈ ፡ ዕዝራ ፥ ምዕራፍ ፡ 2 ።

ምዕራፍ ፡ 2 ።

1 ፤ የባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆር ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ከማረካቸው ፡ ምርኮኛዎች ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምና ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ ወደ ፡ እየከተማቸው ፡ የተመለሱት ፡ የአገር ፡ ልጆች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ።

2 ፤ ከዘሩባቤል ፥ ከኢያሱ ፥ ከነሐምያ ፥ ከሰራያ ፥ ከረዕላያ ፥ ከመርዶክዮስ ፥ ከበላሳን ፥ ከመሴፋር ፥ ከበጉዋይ ፥ ከሬሁም ፥ ከበዓና ፡ ጋራ ፡ መጡ ።

3 ፤ የእስራኤልም ፡ ሕዝብ ፡ ሰዎች ፡ ቍጥር ፡ ይህ ፡ ነው ፤ የፋሮስ ፡ ልጆች ፥ ኹለት ፡ ሺሕ ፡ መቶ ፡ ሰባ ፡ ኹለት ።

4 ፤ የሰፋጥያስ ፡ ልጆች ፥ ሦስት ፡ መቶ ፡ ሰባ ፡ ኹለት ።

5 ፤ የኤራ ፡ ልጆች ፥ ሰባት ፡ መቶ ፡ ሰባ ፡ ዐምስት ።

6 ፤ ከኢያሱና ፡ ከኢዮአብ ፡ ልጆች ፡ የኾኑ ፡ የፈሐት ፡ ሞዐብ ፡ ልጆች ፥ ኹለት ፡ ሺሕ ፡ ስምንት ፡ መቶ ፡ ዐሥራ ፡ ኹለት ።

7 ፤ የዔላም ፡ ልጆች ፥ ሺሕ ፡ ኹለት ፡ መቶ ፡ ዐምሳ ፡ አራት ።

8 ፤ የዛቱዕ ፡ ልጆች ፥ ዘጠኝ ፡ መቶ ፡ አርባ ፡ ዐምስት ።

9 ፤ የዘካይ ፡ ልጆች ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ስድሳ ።

10 ፤ የባኒ ፡ ልጆች ፥ ስድስት ፡ መቶ ፡ አርባ ፡ ኹለት ።

11 ፤ የቤባይ ፡ ልጆች ፥ ስድስት ፡ መቶ ፡ ኻያ ፡ ሦስት ።

12 ፤ የዓዝጋድ ፡ ልጆች ፥ ሺሕ ፡ ኹለት ፡ መቶ ፡ ኻያ ፡ ኹለት ።

13 ፤ የአዶኒቃም ፡ ልጆች ፥ ስድስት ፡ መቶ ፡ ስድሳ ፡ ስድስት ።

14 ፤ የበጉዋይ ፡ ልጆች ፥ ኹለት ፡ ሺሕ ፡ ዐምሳ ፡ ስድስት ።

15 ፤ የዓዲን ፡ ልጆች ፥ አራት ፡ መቶ ፡ ዐምሳ ፡ አራት ።

16 ፤ ከሕዝቅያስ ፡ ወገን ፡ የአጤር[232] ፡ ልጆች ፥ ዘጠና ፡ ስምንት ።

17 ፤ የቤሳይ ፡ ልጆች ፥ ሦስት ፡ መቶ ፡ ኻያ ፡ ሦስት ።

18 ፤ የዮራ ፡ ልጆች ፥ መቶ ፡ ዐሥራ ፡ ኹለት ።

19 ፤ የሐሱም ፡ ልጆች ፥ ኹለት ፡ መቶ ፡ ኻያ ፡ ሦስት ።

20 ፤ 21 ፤ የጋቤር ፡ ልጆች ፥ ዘጠና ፡ ዐምስት ። የቤተ ፡ ልሔም ፡ ልጆች ፥ መቶ ፡ ኻያ ፡ ሦስት ።

22 ፤ የነጦፋ ፡ ሰዎች ፥ ዐምሳ ፡ ስድስት ።

23 ፤ የዐናቶት ፡ ሰዎች ፥ መቶ ፡ ኻያ ፡ ስምንት ።

24 ፤ የዓዝሞት ፡ ልጆች ፥ አርባ ፡ ኹለት ።

25 ፤ የቂርያትይዓሪምና ፡ የከፊራ ፡ የብኤሮትም ፡ ልጆች ፥ ሰባት ፡ መቶ ፡ አርባ ፡ ሦስት ።

26 ፤ የራማና ፡ የጌባ ፡ ልጆች ፥ ስድስት ፡ መቶ ፡ ኻያ ፡ አንድ ።

27 ፤ የማክማስ ፡ ሰዎች ፥ መቶ ፡ ኻያ ፡ ኹለት ።

28 ፤ የቤቴልና ፡ የጋይ ፡ ሰዎች ፥ ኹለት ፡ መቶ ፡ ኻያ ፡ ሦስት ።

29 ፤ የናባው ፡ ልጆች ፥ ዐምሳ ፡ ኹለት ።

30 ፤ የመጌብስ ፡ ልጆች ፥ መቶ ፡ ዐምሳ ፡ ስድስት ።

31 ፤ የኹለተኛውም ፡ ዔላም ፡ ልጆች ፥ ሺሕ ፡ ኹለት ፡ መቶ ፡ ዐምሳ ፡ አራት ።

32 ፤ የካሪም ፡ ልጆች ፥ ሦስት ፡ መቶ ፡ ኻያ ።

33 ፤ የሎድና ፡ የሐዲድ ፡ የኦኖም ፡ ልጆች ፥ ሰባት ፡ መቶ ፡ ኻያ ፡ ዐምስት ።

34 ፤ የኢያሪኮ ፡ ልጆች ፥ ሦስት ፡ መቶ ፡ አርባ ፡ ዐምስት ።

35 ፤ የሴናዓ ፡ ልጆች ፥ ሦስት ፡ ሺሕ ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ።

36 ፤ ካህናቱ ፤ ከኢያሱ ፡ ወገን ፡ የዮዳዔ ፡ ልጆች ፥ ዘጠኝ ፡ መቶ ፡ ሰባ ፡ ሦስት ።

232ዕብ. ፥ አጤር ፡ (ሐጹር ፥ ቅጡር • የታጠረ) ።

37 ፤ የኢሜር ፡ ልጆች ፥ ሺሕ ፡ ዐምሳ ፡ ኹለት ።

38 ፤ የፋስኮር ፡ ልጆች ፥ ሺሕ ፡ ኹለት ፡ መቶ ፡ አርባ ፡ ሰባት ።

39 ፤ የካሪም ፡ ልጆች ፥ ሺሕ ፡ ዐሥራ ፡ ሰባት ።

40 ፤ ሌዋውያኑ ፤ ከሆዳይዋ ፡ ወገን ፡ የኢያሱና ፡ የቀድምኤል ፡ ልጆች ፥ ሰባ ፡ አራት ።

41 ፤ መዘምራኑ ፤ የአሣፍ ፡ ልጆች ፥ መቶ ፡ ኻያ ፡ ስምንት ።

42 ፤ የበረኛዎች ፡ ልጆች ፤ የሰሎም ፡ ልጆች ፥ የአጤር ፡ ልጆች ፥ የጤልሞን ፡ ልጆች ፥ የዐቁብ ፡ ልጆች ፥ የሐጢጣ ፡ ልጆች ፥ የሰባይ ፡ ልጆች ፥ ኹሉ ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ዘጠኝ ።

43 ፤ ናታኒም ፤ የሲሐ ፡ ልጆች ፥ የሐሡፋ ፡ ልጆች ፥

44 ፤ የጠብዖት ፡ ልጆች ፥ የኬራስ ፡ ልጆች ፥ የሲዓ[233] ፡ ልጆች ፤

45 ፤ የፋዶን ፡ ልጆች ፥ የልባና ፡ ልጆች ፥

46 ፤ የአጋባ ፡ ልጆች ፥ የዐቁብ ፡ ልጆች ፥ የአጋብ ፡ ልጆች ፥ የሰምላይ ፡ ልጆች ፥ የሐናን ፡ ልጆች ፥

47 ፤ የጌዴል ፡ ልጆች ፥ የጋሐር ፡ ልጆች ፥ የራያ ፡ ልጆች ፥

48 ፤ የረአሶን ፡ ልጆች ፥ የኔቆዳ ፡ ልጆች ፥

49 ፤ የጋሴም ፡ ልጆች ፥ የዖዛ ፡ ልጆች ፥ የፋሴሐ ፡ ልጆች ፥

50 ፤ የቤሳይ ፡ ልጆች ፥ የአስና ፡ ልጆች ፥ የምዑናውያን ፡ ልጆች ፥ የንፉሰሲም ፡ ልጆች ፥

51 ፤ የበቅቡቅ ፡ ልጆች ፥ የሐቁፋ ፡ ልጆች ፥ የሐርሑር ፡ ልጆች ፥

52 ፤ የበስሎት ፡ ልጆች ፥ የምሒዳ ፡ ልጆች ፥

53 ፤ የሐርሳ ፡ ልጆች ፥ የበርቆስ ፡ ልጆች ፥

54 ፤ የሢሣራ ፡ ልጆች ፥ የቴማ ፡ ልጆች ፥ የንስያ ፡ ልጆች ፥ የሐጢፋ ፡ ልጆች ።

55 ፤ የሰሎሞንም ፡ ባሪያዎች ፡ ልጆች ፤ የሶጣይ ፡ ልጆች ፥ የሶፌሬት ፡ ልጆች ፥ የፍሩዳ ፡ ልጆች ፥

56 ፤ የየዕላ ፡ ልጆች ፥ የደርቆን ፡ ልጆች ፥ የጌዴል ፡ ልጆች ፥

57 ፤ የሰፋጥያስ ፡ ልጆች ፥ የሐጢል ፡ ልጆች ፥ የፈከራት ፡ ልጆች ፥ የሐፂቦይም ፡ ልጆች ፥ የአሚ ፡ ልጆች ።

58 ፤ እነዚህ ፡ ናታኒም ፡ ኹሉና ፡ የሰሎሞን ፡ ባሪያዎች ፡ ልጆች ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ዘጠና ፡ ኹለት ፡ ነበሩ ።

59 ፤ ከቴልሜላ ፥ ከቴላሬሳ ፥ ከክሩብ ፥ ከአዳን ፥ ከኢሜር ፡ የወጡ ፡ እነዚህ ፡ ነበሩ ፤ ነገር ፡ ግን ፥ የአባቶቻቸውን ፡ ቤቶችና ፡ ዘራቸውን ፡ ወይም ፡ ከእስራኤል ፡ ወገን ፡ መኾናቸውን ፡ ያስታውቁ ፡ ዘንድ ፡ አልቻሉም ፤

60 ፤ የዳላያ ፡ ልጆች ፥ የጦብያ ፡ ልጆች ፥ የኔቆዳ ፡ ልጆች ፥ ስድስት ፡ መቶ ፡ ዐምሳ ፡ ኹለት ፡ ነበሩ ።

61 ፤ ከካህናቱም ፡ ልጆች ፤ የኤብያ ፡ ልጆች ፥ የአቆስ ፡ ልጆች ፥ ከገለዓዳዊው ፡ ከቤርዜሊ ፡ ልጆች ፡ ሚስት ፡ ያገባ ፥ በስሙም ፡ የተጠራ ፡ የቤርዜሊ ፡ ልጆች ።

62 ፤ እነዚህ ፡ በትውልድ ፡ መጽሐፍ ፡ ትውልዳቸውን ፡ ፈለጉ ፤ ነገር ፡ ግን ፥ አልተገኘም ፥ ከክህነትም ፡ ተከለከሉ ።

63 ፤ ሐቴርሰታም ፦ በኡሪምና ፡ በቱሚም ፡ የሚፈርድ ፡ ካህን ፡ እስኪነሣ ፡ ድረስ ፡ ከቅዱስ ፡ ቅዱሳን ፡ አትበሉም ፡ አላቸው ።

64 ፤ 65 ፤ ሰባት ፡ ሺሕ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ሰባት ፡ ከነበሩ ፡ ከሎሌዎቻቸውና ፡ ከገረዶቻቸው ፡ ሌላ ፡ ጉባኤው ፡ ኹሉ ፡ አርባ ፡ ኹለት ፡ ሺሕ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ስድሳ ፡ ነበሩ ። ኹለት ፡ መቶም ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ መዘምራን ፡ ነበሯቸው ።

233 ዕብ. ፥ ጺሓ ፡ (ጽሕው • የጠራ ፥ የበራ ፥ ቊልጭ ፡ ያለ) ።

66 ፤ ፈረሶቻቸውም ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ስድስት ፡ በቅሎዎቻቸውም ፡ ኹለት ፡ መቶ ፡ አርባ ፡ ዐምስት ፥

67 ፤ ግመሎቻቸውም ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ዐምስት ፥ አህያዎቻቸውም ፡ ስድስት ፡ ሺሕ ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ኻያ ፡ ነበሩ ።

68 ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ ወዳለው ፡ ወደእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ ከአባቶች ፡ ቤቶች ፡ አለቃዎች ፡ ዐያሌዎች ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ በስፍራው ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ በፈቃዳቸው ፡ ሰጡ ።

69 ፤ ስድሳ ፡ አንድ ፡ ሺሕም ፡ የወርቅ ፡ ዳሪክ ፥ ዐምስት ፡ ሺሕም ፡ ምናን ፡ ብር ፥ አንድ ፡ መቶም ፡ የካህናት ፡ ልብስ ፡ እንደ ፡ ችሎታቸው ፡ ወደሥራው ፡ ቤተ ፡ መዛግብት ፡ አቀረቡ ።

70 ፤ ካህናቱና ፡ ሌዋውያኑም ፥ ከሕዝቡም ፡ ዐያሌዎች ፥ መዘምራኑና ፡ በረኛዎቹም ፥ ናታኒምም ፡ በከተማዎቻቸው ፥ እስራኤልም ፡ ኹሉ ፡ በከተማዎቻቸው ፡ ተቀመጡ ።

## መጽሐፈ ፡ ዕዝራ ፥ ምዕራፍ ፡ 3 ።

ምዕራፍ ፡ 3 ።

1 ፤ ሰባተኛውም ፡ ወር ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፥ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በከተማዎቻቸው ፡ ሳሉ ፥ ሕዝቡ ፡ እንደ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ኾነው ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ተሰበሰቡ ።

2 ፤ የኢዮሴዴቅም ፡ ልጅ ፡ ኢያሱ ፥ ወንድሞቹም ፡ ካህናቱ ፥ የሰላትያልም ፡ ልጅ ፡ ዘሩባቤል ፡ ወንድሞቹም ፡ ተነሥተው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ በሙሴ ፡ ሕግ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፡ ያቀርቡበት ፡ ዘንድ ፡ የእስራኤልን ፡ አምላክ ፡ መሠዊያ ፡ ሠሩ ።

3 ፤ በአገሩም ፡ ካሉት ፡ አሕዛብ ፡ ፈርተው ፡ ነበርና ፥ መሠዊያውን ፡ በስፍራው ፡ ላይ ፡ አስቀመጡት ፥ በጧትና ፡ በማታም ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አቀረቡበት ።

4 ፤ እንደተጻፈውም ፡ የዳስ ፡ በዓል ፡ አደረጉ ፤ እንደ ፡ ሥርዐቱም ፡ ለየዕለቱ ፡ የተገባውን ፡ የየዕለቱን ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ በቍጥር ፡ አቀረቡ ።

5 ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ዘወትር ፡ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕት ፥ የመባቻውንም ፡ መሥዋዕት ፥ የተቀደሱትንም ፡ የእግዚአብሔር ፡ በዓላት ፡ ኹሉ ፡ መሥዋዕት ፥ ሰውም ፡ ኹሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በፈቃድ ፡ የሰጠውን ፡ ቍርባን ፡ አቀረቡ ።

6 ፤ በሰባተኛው ፡ ወር ፡ በመዠመሪያው ፡ ቀን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ማቅረብ ፡ ዠመሩ ፤ የእግዚአብሔር ፡ መቅደስ ፡ ገና ፡ አልተመሠረተም ፡ ነበር ።

7 ፤ ለጠራቢዎችና ፡ ለዐናጢዎችም ፡ ገንዘብ ፡ ሰጡ ፤ የፋርስም ፡ ንጉሥ ፡ ቂሮስ ፡ እንደ ፡ ፈቀደላቸው ፡ የዝግባ ፡ ዛፍ ፡ ከሊባኖስ ፡ በባሕር ፡ ወደ ፡ ኢዮጴ ፡ ያመጡ ፡ ዘንድ ፡ ለሲዶናና ፡ ለጢሮስ ፡ ሰዎች ፡ መብልና ፡ መጠጥ ፡ ዘይትም ፡ ሰጡ ።

8 ፤ በኢየሩሳሌም ፡ ወዳለው ፡ ወደእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ በመጡ ፡ በኹለተኛው ፡ ዓመት ፡ በኹለተኛው ፡ ወር ፡ የሰላትያል ፡ ልጅ ፡ ዘሩባቤል ፥ የኢዮሴዴቅም ፡ ልጅ ፡ ኢያሱ ፥ የቀሩትም ፡ ወንድሞቻቸው ፡ ካህናትና ፡ ሌዋውያን ፥ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ የተመለሱት ፡ ምርኮኛዎች ፡ ኹሉ ፡ ዠመሩ ፤ ሌዋውያንንም ፡ ከኻያ ፡ ዓመት ፡ ዠምሮ ፡ ከዚያም ፡ በላይ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ሥራ ፡ እንዲያሠሩት ፡ ሾሟቸው ።

9 ፤ ኢያሱም ፡ ልጆቹም ፡ ወንድሞቹም ፥ የይሁዳም ፡ ልጆች ፡ ቀድምኤልና ፡ ልጆቹ ፥ የኤንሐዳድም ፡ ልጆች ፥ ልጆቻቸውና ፡ ወንድሞቻቸው ፡ ሌዋውያንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ የሚሠሩትን ፡ ያሠሩ ፡ ዘንድ ፡ በአንድነት ፡ ቆሙ ።

10 ፤ ዐናጢዎቹም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መቅደስ ፡ በመሠረቱ ፡ ጊዜ ፡ ካህናቱ ፡ ልብሳቸውን ፡ ለብሰው ፡ መለከቱን ፡ ይዘው ፥ የአሳፍም ፡ ልጆች ፡ ሌዋውያን ፡ ጸናጽል ፡ ይዘው ፡ እንደ ፡ እስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ እንደ ፡ ዳዊት ፡ ሥርዐት ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመሰግኑ ፡ ዘንድ ፡ ቆሙ ።

11 ፤ ደግሞ ፦ ቸር ፡ ነውና ፥ ለእስራኤልም ፡ ምሕረቱ ፡ ለዘለዓለም ፡ ነውና ፥ እያሉ ፡ እግዚአብሔርንም ፡ እያመሰገኑና ፡ እያከበሩ ፡ ርስ ፡ በርሳቸው ፡ ያስተዛዝሉ ፡ ነበር ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ ስለ ፡ ተመሠረተ ፡ ሕዝቡ ፡ ኹሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እያመሰገኑ ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ እልል ፡ አሉ ።

12 ፤ የፊተኛውን ፡ ቤት ፡ ያዩ ፡ ሽማግሌዎች ፡ የኾኑ ፡ ብዙ ፡ ካህናትና ፡ ሌዋውያን ፡ የአባቶችም ፡ ቤቶች ፡ አለቃዎች ፡ ግን ፡ ይህ ፡ መቅደስ ፡ በፊታቸው ፡ በተመሠረተ ፡ ጊዜ ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ ያለቅሱ ፡ ነበር ፤ ብዙ ፡ ሰዎችም ፡ በደስታ ፡ ይጮኹ ፡ ነበር ፤

13 ፤ ደስ ፡ ብሏቸው ፡ የሚጮኹትን ፡ ድምፅ ፡ ከሕዝቡ ፡ ልቅሶ ፡ ድምፅ ፡ መለየት ፡ የሚችል ፡ አልነበረም ፤ ሕዝቡም ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ ይጮኽ ፡ ነበር ፥ ድምፁም ፡ ከሩቅ ፡ ይሰማ ፡ ነበር ።

## መጽሐፈ ፡ ዕዝራ ፥ ምዕራፍ ፡ 4 ።

ምዕራፍ ፡ 4 ።

1 ፤ የይሁዳና ፡ የብንያምም ፡ ጠላቶች ፡ ምርኮኞዎቹ ፡ ለእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መቅደስ ፡ እንደ ፡ ሠሩ ፡ ሰሙ ።

2 ፤ ወደ ፡ ዘሩባቤልና ፡ ወዳባቶች ፡ ቤቶች ፡ አለቃዎች ፡ ቀርበው ፦ የአሶር ፡ ንጉሥ ፡ አስራዶን ፡ ወደዚህ ፡ ካመጣን ፡ ቀን ፡ ዠምሮ ፡ ለአምላካችኹ ፡ እንሠዋለንና ፥ እንደናንተም ፡ እንፈልገዋለንና ፡ ከእናንተ ፡ ጋራ ፡ እንሥራ ፡ አሏቸው ።

3 ፤ ዘሩባቤልና ፡ ኢያሱም ፡ የቀሩትም ፡ የእስራኤል ፡ አባቶች ፡ ቤቶች ፡ አለቃዎች ፦ የአምላካችንን ፡ ቤት ፡ መሥራት ፡ ለእኛና ፡ ለእናንተ ፡ አይደለም ፤ እኛ ፡ ለብቻችን ፡ ግን ፡ የፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ ቂሮስ ፡ እንዳዘዘን ፡ ለእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ እንሠራለን ፡ አሏቸው ።

4 ፤ የምድሩም ፡ ሕዝብ ፡ የይሁዳን ፡ ሕዝብ ፡ እጅ ፡ ያደክሙ ፡ ነበር ፥ እንዳይሠሩም ፡ አስፈራሯቸው ፥

5 ፤ ምክራቸውንም ፡ ያፈርሱ ፡ ዘንድ ፡ በፋርሱ ፡ ንጉሥ ፡ በቂሮስ ፡ ዘመን ፡ ዅሉ ፡ እስከፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ እስከዳርዮስ ፡ መንግሥት ፡ ድረስ ፡ መካሪዎችን ፡ ገዙባቸው ።

6 ፤ በአርጤክስስ[234]ም ፡ መንግሥት ፥ በመንግሥቱም ፡ በመዠመሪያ ፡ ዘመን ፥ በይሁዳና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ በሚኖሩት ፡ ላይ ፡ የክስ ፡ ነገር ፡ ጻፉ ።

7 ፤ በአርጤክስስ ፡ ዘመን ፡ ቢሽላም ፥ ሚትሪዳጡ ፥ ጣብኤል ፡ ተባባሪዎቹም ፡ ለፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ ለአርጤክስስ ፡ ጻፉ ፤ ደብዳቤውም ፡ በሶርያ ፡ ፊደልና ፡ በሶርያ ፡ ቋንቋ ፡ ተጽፎ ፡ ነበር ።

8 ፤ አዛዡ ፡ሬሁም ፡ ጸሓፊውም ፡ ሲምሳይ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ላይ ፡ ለንጉሡ ፡ ለአርጤክስስ ፡ እንዲህ ፡ የሚል ፡ ደብዳቤ ፡ ጻፉ ።

9 ፤ አዛዡ ፡ ሬሁም ፥ ጸሓፊውም ፡ ሲምሳይ ፥ የቀሩትም ፡
ተባባሪዎቻቸው ፥ ዲናውያን ፣ አፈርሣትካውያን ፣ ጠርፈላውያን ፣ አፈርሣውያን ፣ አርካውያን ፣ ባቢሎናውያን ፣ ሱስናካውያን ፣ ዴሐውያን ፣ ኤላማውያን ፥

10 ፤ ታላቁና ፡ ኀይለኛው ፡ አስናፈር ፡ ያፈለሳቸው ፡ በሰማርያና ፡ በወንዝ ፡ ማዶ ፡ ያኖራቸው ፡ የቀሩትም ፡ አሕዛብ ፡ ደብዳቤውን ፡ ጻፉ ።

11 ፤ ለንጉሡ ፡ ለአርጤክስስ ፡ የላኩት ፡ የደብዳቤ ፡ ግልባጭ ፡ ይህ ፡ ነው ፦ በወንዝ ፡ ማዶ ፡ ያሉት ፡ ሰዎች ፡ ባሪያዎችኽ ፤

12 ፤ አኹንም ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡ የወጡ ፡ አይሁድ ፡ ወደ ፡ እኛ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ እንደ ፡ መጡ ፡ ንጉሡ ፡ ይወቅ ፤ ዐመፀኛዪቱንና ፡ እጅግም ፡ የከፋቺቱን ፡ ከተማ ፡ ይሠራሉ ፥ ቅጥሯንም ፡ ያድሳሉ ፥ መሠረቷንም ፡ ጠገኑ ።

13 ፤ አኹንም ፡ ይህች ፡ ከተማ ፡ የተሠራች ፡ እንደ ፡ ኾነ ፥ ቅጥሯም ፡ የታደሰ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፥ ግብርና ፡ ቀረጥ ፡ መጥንም ፡ እንዳይሰጡ ፥ የንጉሡም ፡ ግቢው ፡ እንዲጐድል ፡ ንጉሡ ፡ ይወቅ ።

14 ፤ የንጉሡንም ፡ ጨው ፡ እንበላለንና ፥ ንጉሡንም ፡ ሲያቃልሉት ፡ ማየት ፡ አይገባንምና ፡ ስለዚህ ፡ ልከን ፡ ለንጉሡ ፡ አስታውቀናል ፤

15 ፤ በአባቶችኽ ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ ምርመራ ፡ ይደረግ ፤ በዚያም ፡ በታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ ይህች ፡ ከተማ ፡ ዐመፀኛ ፡

234ዕብ. ፥ አሐሽቬሮሽ ።

እንደ ፡ ኾነች ፤ ነገሥታትንና ፡ አውራጃዎችንም ፡ እንደ ፡ ጐዳች ፤ ከጥንቱም ፡ ሽፍትነት ፡ በርሷ ፡ እንደ ፡ ተገኘመረ ፡ ታገኛለኽ ፤ ታውቃለኽም ፤ ስለዚህም ፡ ይህች ፡ ከተማ ፡ ፈርሳ ፡ ነበር ።

16 ፤ ይህችም ፡ ከተማ ፡ የተሠራች ፡ እንደ ፡ ኾነ ፤ ቅጥሯም ፡ የታደሰ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፤ በወንዝ ፡ ማዶ ፡ ክፍል ፡ እንደሌለኽ ፡ ለንጉሡ ፡ እናስታውቃለን ።

17 ፤ ንጉሡም ፡ ለአዛዡ ፡ ለሬሁም ፤ ለጸሓፊውም ፡ ለሲምሳይ ፤ በሰማርያና ፡ በወንዝ ፡ ማዶም ፡ ለተቀመጡ ፡ ለቀሩት ፡ ተባባሪዎቻቸው ፡ እንዲህ ፡ የሚለውን ፡ መልስ ፡ ላከ ፦

18 ፤ ሰላም ፤ አኹንም ፡ ወደ ፡ እኛ ፡ የላካችኹት ፡ ደብዳቤ ፡ በፊቴ ፡ ተተርጒሞ ፡ ተነበበ ።

19 ፤ እኔም ፡ አዝገኘለኹ ፤ ተመረመረም ፤ ይህችም ፡ ከተማ ፡ ከጥንት ፡ ዠምራ ፡ በነገሥታት ፡ ላይ ፡ ዐመፀኛ ፡ እንደ ፡ ነበረች ፤ በርሷም ፡ ዐመፅና ፡ ሽፍትነት ፡ እንደ ፡ ተደረገ ፡ ተገኘ ።

20 ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ እጅግ ፡ ኀያላን ፡ ነገሥታት ፡ ነበሩ ፤ በወንዝም ፡ ማዶ ፡ ያለውን ፡ አገር ፡ ኹሉ ፡ ይገዙ ፡ ነበር ፤ ግብርንና ፡ ቀረጥን ፡ መጥንንም ፡ ይቀበሉ ፡ ነበር ።

21 ፤ አኹንም ፡ እነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ሥራውን ፡ እንዲተዉ ፤ እኔም ፡ እስካዝ ፡ ድረስ ፡ ይህች ፡ ከተማ ፡ እንዳትሠራ ፡ ትእዛዝ ፡ ስጡ ።

22 ፤ ቸልም ፡ እንዳትሉ ፡ ተጠንቀቁ ፤ ለነገሥታቱ ፡ ጒዳትና ፡ ጥፋት ፡ እየበዛ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ይኼዳል ፧

23 ፤ የንጉሡም ፡ የአርጤክስስ ፡ ደብዳቤ ፡ ግልባጭ ፡ በሬሁምና ፡ በጸሓፊው ፡ በሲምሳይ ፡ በተባባሪዎቻቸውም ፡ ፊት ፡ በተነበበ ፡ ጊዜ ፤ ፈጥነው ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወደ ፡ አይሁድ ፡ ኼዱ ፤ በግድና ፡ በኀይልም ፡ አስተዉአቸው ።

24 ፤ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ያለው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ሥራ ፡ ቀረ ፤ እስከፋርስም ፡ ንጉሥ ፡ እስከዳርዮስ ፡ መንግሥት ፡ እስከ ፡ ኹለተኛው ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡ ተጓጐለ ።

______________መጽሐፈ ፡ ዕዝራ ፤ ምዕራፍ ፡ 5 ። ______________

ምዕራፍ ፡ 5 ።

1 ፤ ነቢያቱም ፡ ሐጌና ፡ የአዶ ፡ ልጅ ፡ ዘካርያስ ፡ በይሁዳና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ለነበሩ ፡ አይሁድ ፡ በእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ስም ፡ ትንቢት ፡ ተናገሩላቸው ።

2 ፤ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ የሰላትያል ፡ ልጅ ፡ ዘሩባቤል ፡ የኢዮሴዴቅም ፡ ልጅ ፡ ኢያሱ ፡ ተነሥተው ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ያለውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ መሥራት ፡ ዠመሩ ፤ የሚያግዟቸውም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ነቢያት ፡ ከነርሱ ፡ ጋራ ፡ ነበሩ ።

3 ፤ በዚያም ፡ ዘመን ፡ በወንዝ ፡ ማዶ ፡ የነበረው ፡ ገዥ ፡ ተንትናይ ፤ ደግሞ ፡ ሰተርቡዝናይ ፤ ተባባሪዎቻቸውም ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ መጥተው ፦ ይህን ፡ ቤት ፡ ትሠሩ ፡ ዘንድ ፤ ይህንኑም ፡ ቅጥር ፡ ታድሱ ፡ ዘንድ ፡ ያዘዛችኹ ፡ ማን ፡ ነው ፧ አሏቸው ።

4 ፤ ደግሞም ፦ ይህንስ ፡ ሥራ ፡ የሚሠሩት ፡ ሰዎች ፡ ስም ፡ ማን ፡ ነው ፧ ብለው ፡ ጠየቋቸው ።

5 ፤ የአምላካቸው ፡ ዐይን ፡ ግን ፡ በአይሁድ ፡ ሽማግሌዎች ፡ ላይ ፡ ነበረ ፤ ይህም ፡ ነገር ፡ ወደ ፡ ዳርዮስ ፡ እስኪደርስ ፡ ድረስ ፤ መልሱም ፡ በደብዳቤ ፡ እስኪመጣ ፡ ድረስ ፡ አልከለከሏቸውም ።

6 ፤ በወንዙ ፡ ማዶ ፡ የነበረው ፡ ገዥ ፡ ተንትናይ ፡ ደግሞ ፡ ሰተርቡዝናይ ፡ ተባባሪዎቹም ፡ በወንዙ ፡ ማዶ ፡ የነበሩት ፡ አፈርሥካውያን ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ዳርዮስ ፡ የላኩት ፡ የደብዳቤው ፡ ግልባጭ ፡ ይህ ፡ ነበረ ።

7 ፤ እንዲህም ፡ የሚል ፡ ደብዳቤ ፡ ላኩለት ፦ ለንጉሡ ፡ ለዳርዮስ ፡ ሙሉ ፡ ሰላም ፡ ይኹን ፤

8 ፤ ወደይሁዳ ፡ አገር ፡ ወደታላቁም ፡ አምላክ ፡ ቤት ፡ እንደ ፡ ኼድን ፡ ንጉሡ ፡ ይወቅ ፤ ርሱም ፡ በትልቅ ፡ ድንጋይ ፡ ተሠራ ፤ በቅጥሩም ፡ ውስጥ ፡ ዕንጨት ፡ ተደረገ ፤ ያም ፡ ሥራ ፡ በትጋት ፡ ይሠራል ፤ በእጃቸውም ፡ ይከናወናል ።

9 ፤ እነዚያንም ፡ ሽማግሌዎች ፦ ይህን ፡ ቤት ፡ ትሠሩ ፡ ዘንድ ፤ ይህንስ ፡ ቅጥር ፡ ታድሱ ፡ ዘንድ ፡ ያዘዛችኹ ፡ ማን ፡ ነው ፧ ብለን ፡ ጠየቅናቸው ።

10 ፤ ደግሞም ፡ እናስታውቅኽ ፡ ዘንድ ፥ በእነርሱም ፡ ያሉትን ፡ ሹሞች ፡ ስም ፡ እንጽፍልኽ ፡ ዘንድ ፡ ስማቸውን ፡ ጠየቅን ።

11 ፤ እንደዚህም ፡ ብለው ፡ መለሱልን ፦ እኛ ፡ የሰማይና ፡ የምድር ፡ አምላክ ፡ ባሪያዎች ፡ ነን ፥ ከብዙም ፡ ዘመን ፡ ዠምሮ ፡ ተሠርቶ ፡ የነበረውን ፥ ታላቁም ፡ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ሠርቶ ፡ የፈጸመውን ፡ ቤት ፡ እንሠራለን ።

12 ፤ አባቶቻችንም ፡ የሰማይን ፡ አምላክ ፡ ካስቈጡ ፡ በዃላ ፡ በከለዳዊው ፡ በባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ በናቡከደነጾር ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣቸው ፥ ርሱም ፡ ይህን ፡ ቤት ፡ አፈረሰ ፥ ሕዝቡንም ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ አፈለሰ ።

13 ፤ ነገር ፡ ግን ፥ በባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ በቂሮስ ፡ በመዠመሪያው ፡ ዓመት ፡ ንጉሡ ፡ ቂሮስ ፡ ይህን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ።

14 ፤ ናቡከደነጾርም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ከነበረው ፡ መቅደስ ፡ የወሰደውን ፥ ወደባቢሎንም ፡ መቅደስ ፡ ያፈለሰውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ የወርቅንና ፡ የብርን ፡ ዕቃ ፡ ንጉሡ ፡ ቂሮስ ፡ ከባቢሎን ፡ መቅደስ ፡ አውጥቶ ፡ ሰሳብሳር ፡ ለተባለው ፡ ለሹሙ ፡ ሰጠውና ፦

15 ፤ ይህን ፡ ዕቃ ፡ ይዘኽ ፡ ኺድ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ ባለው ፡ መቅደስ ፡ አኑረው ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ በስፍራው ፡ ይሠራ ፡ አለው ።

16 ፤ በዚያ ፡ ጊዜም ፡ ይህ ፡ ሰሳብሳር ፡ መጣ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ ያለውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ መሠረተ ፤ ከዚያም ፡ ጊዜ ፡ ዠምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ እየተሠራ ፡ አልተጨረሰም ።

17 ፤ አኹንም ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ በንጉሡ ፡ ዐይን ፡ መልካም ፡ ቢኾን ፡ ይህ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ ከንጉሡ ፡ ከቂሮስ ፡ ታዞ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ በባቢሎን ፡ ባለው ፡ በንጉሡ ፡ ቤተ ፡ መዛግብት ፡ ይመርመር ፤ ስለዚህም ፡ ነገር ፡ ንጉሡ ፡ ፈቃዱን ፡ ይላክልን ።

_______________መጽሐፈ ፡ ዕዝራ ፥ ምዕራፍ ፡ 6 ። _______________

ምዕራፍ ፡ 6 ።

1 ፤ በዚያ ፡ ጊዜም ፡ ንጉሡ ፡ ዳርዮስ ፡ መዛግብት ፡ ባሉበት ፡ በባቢሎን ፡ ቤት ፡ መጻሕፍት ፡ እንዲመረመር ፡ አዘዘ ።

2 ፤ በሜዶን ፡ አውራጃ ፡ ባለው ፡ አሕምታ ፡ በሚባል ፡ ከተማ ፡ በንጉሡ ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ አንድ ፡ ጥቅል ፡ ተገኘ ፥ በውስጡም ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ ለመታሰቢያ ፡ ተጽፎ ፡ ነበር ።

3 ፤ በንጉሡ ፡ በቂሮስ ፡ በመዠመሪያው ፡ ዓመት ፡ ንጉሡ ፡ ቂሮስ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ አዘዘ ፤ በኢየሩሳሌም ፡ ያለው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቤት ፥ መሥዋዕት ፡ የሚቀርብበት ፡ ቦታ ፥ ይህ ፡ ቤት ፡ ይሠራ ፥ በጽኑም ፡ ይመሥረት ፤ ቁመቱ ፡ ስድሳ ፡ ክንድ ፡ ወርዱም ፡ ስድሳ ፡ ክንድ ፡ ይኹን ።

4 ፤ በሦስት ፡ ተራ ፡ ታላላቅ ፡ ድንጋይ ፥ ባንድ ፡ ተራ ፡ ዕንጨት ፡ ይደረግ ፤ ውጪውም ፡ ከንጉሡ ፡ ቤት ፡ ይሰጥ ።

5 ፤ ናቡከደነጾርም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ካለው ፡ መቅደስ ፡ ወስዶ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ያመጣው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ የወርቅና ፡ የብር ፡ ዕቃ ፡ ይመለስ ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ ወዳለው ፡ መቅደስ ፡ ወደ ፡ ስፍራው ፡ ይወሰድ ፥ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ይኑር ።

6 ፤ አኹንም ፡ አንተ ፡ በወንዝ ፡ ማዶ ፡ ያለኸው ፡ የአገሩ ፡ ገዢ ፡ ተንትናይ ፡ ደግሞ ፡ ሰተርቡዝናይ ፡ በወንዝ ፡ ማዶም ፡ ያሉ ፡ ተባባሪዎቻችኹ ፡ አፈርሥካውያን ፥ ከዚያ ፡ ራቁ ፤

7 ፤ ይህም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ ተዉ ፤ የአይሁድም ፡ አለቃና ፡ የአይሁድም ፡ ሽማግሌዎች ፡ ይህን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ በስፍራው ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ተዉአቸው ።

8 ፤ ይህን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ለአይሁድ ፡ ሽማግሌዎች ፡ የምታደርጉትን ፥ በወንዝ ፡ ማዶ ፡ ካለው ፡ አገር ፡ ከሚመጣው ፡ ግብር ፡ ከንጉሡ ፡ ገንዘብ ፡ ለእነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ወጪውን ፡ በትጋት ፡ እንድትሰጧቸው ፡ ሥራም ፡ እንዳታስፈቷቸው ፡ አዝዣለኹ ።

9 ፤ ለሰማይ ፡ አምላክ ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ የሚያስፈልገውን ፥ ወይፈኖችና ፡ አውራ ፡ በጎች ፡

ጠቦቶችም ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ እንዳሉ ፡ እንደ ፡ ካህናቱ ፡ ቃል ፡ ስንዴና ፡ ጨው ፡ የወይን ፡ ጠጅና ፡ ዘይት ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ ያለማቋረጥ ፡ ስጧቸው ።

10 ፤ ይኸውም ፡ ለሰማይ ፡ አምላክ ፡ ጣፋጭ ፡ ሽቱ ፡ የኾነውን ፡ መሥዋዕት ፡ ያቀረቡ ፡ ዘንድ ፡ ለንጉሡና ፡ ለልጆቹም ፡ ዕድሜ ፡ ይጸልዩ ፡ ዘንድ ፡ ነው ።

11 ፤ ይህንም ፡ ትእዛዝ ፡ የሚለውጥ ፡ ኹሉ ፥ ምሰሶው ፡ ከቤቱ ፡ ተነቅሎ ፡ ርሱ ፡ ይሰቀልበት ፤ ቤቱም ፡ የጕድፍ ፡ መጣያ ፡ ይደረግ ፡ ብዬ ፡ አዝዣለኹ ።

12 ፤ ስሙንም ፡ በዚያ ፡ ያኖረው ፡ አምላክ ፡ ይህን ፡ ይለውጡ ፡ ዘንድ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ያለውንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ያፈርሱት ፡ ዘንድ ፡ እጃቸውን ፡ የሚዘረጉትን ፡ ነገሥታትና ፡ አሕዛብ ፡ ኹሉ ፡ ያጥፋ ። እኔ ፡ ዳርዮስ ፡ ይህን ፡ አዝዣለኹ ፤ በትጋት ፡ ይፈጸም ።

13 ፤ ንጉሡም ፡ ዳርዮስ ፡ እንደ ፡ ላከው ፡ ቃል ፥ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ በወንዝ ፡ ማዶ ፡ ያለ ፡ ገዢ ፡ ተንትናይ ፡ ደግሞ ፡ ሰተርቡዝናይ ፡ ተባባሪዎቻቸውም ፡ እንዲሁ ፡ ተግተው ፡ አደረጉ ።

14 ፤ የአይሁድም ፡ ሽማግሌዎች ፡ በነቢዩ ፡ በሐጌና ፡ በአዶ ፡ ልጅ ፡ በዘካርያስ ፡ ትንቢት ፡ ሠሩ ፡ ተከናወነላቸውም ። እንደ ፡ እስራኤልም ፡ አምላክ ፡ ትእዛዝ ፥ እንደ ፡ ፋርስም ፡ ነገሥታት ፡ እንደ ፡ ቂሮስና ፡ እንደ ፡ ዳርዮስ ፡ እንደ ፡ አርጤክስስም ፡ ትእዛዝ ፡ ሠርተው ፡ ፈጸሙ ።

15 ፤ ይህም ፡ ቤት ፡ በንጉሡ ፡ በዳርዮስ ፡ መንግሥት ፡ በስድስተኛው ፡ ዓመት ፡ አዳር ፡ በሚባል ፡ ወር ፡ በሦስተኛው ፡ ቀን ፡ ተፈጸመ ።

16 ፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፥ ካህናትና ፡ ሌዋውያን ፡ የቀሩትም ፡ ምርኮኛዎች ፥ የዚህን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ቅዳሴ ፡ በደስታ ፡ አደረጉ ።

17 ፤ በዚህም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ቅዳሴ ፡ መቶ ፡ ወይፈኖችና ፡ ኹለት ፡ መቶ ፡ አውራ ፡ በጎች ፡ አራት ፡ መቶም ፡ ጠቦቶች ፡ አቀረቡ ፡ ፤ ስለኀጢአትም ፡ መሥዋዕት ፡ እንደ ፡ እስራኤል ፡ ነገዶች ፡ ቍጥር ፡ ለእስራኤል ፡ ኹሉ ፡ ዐሥራ ፡ ኹለት ፡ አውራ ፡ ፍየሎች ፡ አቀረቡ ።

18 ፤ በሙሴም ፡ መጽሐፍ ፡ እንደተጻፈው ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ባለው ፡ በእግዚአብሔር ፡ አገልግሎት ፡ ላይ ፡ ካህናቱን ፡ በየማዕርጋቸው ፡ ሌዋውያኑም ፡ በየክፍላቸው ፡ አቆሙ ።

19 ፤ ምርኮኛዎቹም ፡ በመዠመሪያው ፡ ወር ፡ በዐሥራ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ ፋሲካውን ፡ አደረጉ ።

20 ፤ ካህናቱና ፡ ሌዋውያኑም ፡ አንድ ፡ ኾነው ፡ ነጽተው ፡ ነበር ፤ ኹሉም ፡ ንጹሓን ፡ ነበሩ ፤ ለምርኮኛዎቹም ፡ ኹሉ ፥ ለወንድሞቻቸውም ፡ ለካህናቱ ፥ ለራሳቸውም ፡ ፋሲካውን ፡ ዐረዱ ።

21 ፤ ከምርኮም ፡ ተመልሰው ፡ የመጡት ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፥ የእስራኤልንም ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ይፈልጉ ፡ ዘንድ ፡ ራሳቸውን ፡ ከምድር ፡ አሕዛብ ፡ ርኵሰት ፡ ለይተው ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ መጥተው ፡ የነበሩት ፡ ኹሉ ፡ በሉ ፤

22 ፤ እግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ አሠኝቷቸዋልና ፥ የእስራኤልንም ፡ አምላክ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ለመሥራት ፡ እጃቸውን ፡ ያጸና ፡ ዘንድ ፡ የአሶርን ፡ ንጉሥ ፡ ልብ ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ መልሷልና ፥ የቂጣውን ፡ በዓል ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ በደስታ ፡ አደረጉ ።

## መጽሐፈ ፡ ዕዝራ ፥ ምዕራፍ ፡ 7 ።

ምዕራፍ ፡ 7 ።

1 ፤ ከዚህም ፡ ነገር ፡ በኋላ ፡ በፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ በአርጤክስስ ፡ መንግሥት ፡ ዕዝራ ፡ የሰራያ ፡ ልጅ ፥

2 ፤ የዐዛርያስ ፡ ልጅ ፥ የኬልቅያስ ፡ ልጅ ፥ የሰሎም ፡ ልጅ ፥ የሳዶቅ ፡ ልጅ ፥ የአኪጦብ ፡ ልጅ ፥

3 ፤ የአማርያ ፡ ልጅ ፥ የዐዛርያስ ፡ ልጅ ፥ የመራዮት ፡ ልጅ ፥

4 ፤ የዘራእያ ፡ ልጅ ፥ የዖዚ ፡ ልጅ ፥ የቡቂ ፡ ልጅ ፥

5 ፤ የአቢሱ ፡ ልጅ ፥ የፊንሐስ ፡ ልጅ ፥ የአልዓዛር ፡ ልጅ ፥ የታላቁ ፡ ካህን ፡ የአሮን ፡ ልጅ ፥ ይህ ፡ ዕዝራ ፡ ከባቢሎን ፡

ወጣ ፤

6 ፤ የእስራኤልም ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሰጠው ፡ በሙሴ ፡ ሕግ ፡ ፈጣን ፡ ጸሓፊ ፡ ነበረ ፤ የአምላኩም ፡
የእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ በርሱ ፡ ላይ ፡ ነበረችና ፡ ንጉሡ ፡ የሻውን ፡ ኹሉ ፡ ሰጠው ።

7 ፤ ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ከካህናቱም ፡ ከሌዋውያኑም ፡ ከመዘምራኑም ፡ ከበረኛዎቹም ፡ ከናታኒምም ፡ በንጉሡ ፡
በአርጤክስስ ፡ በሰባተኛው ፡ ዓመት ፡ ዐያሌዎች ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወጡ ።

8 ፤ በንጉሡም ፡ በሰባተኛው ፡ ዓመት ፡ በዐምስተኛው ፡ ወር ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ደረሰ ።

9 ፤ በመዠመሪያውም ፡ ወር ፡ በአንደኛው ፡ ቀን ፡ ከባቢሎን ፡ ሊወጣ ፡ ዠመረ ፥ መልካሚቱም ፡ የአምላኩ ፡ እጅ ፡
በርሱ ፡ ላይ ፡ ነበረችና ፡ በዐምስተኛ ፡ ወር ፡ በመዠመሪያው ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ደረሰ ።

10 ፤ ዕዝራም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ ይፈልግና ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፥ ለእስራኤልም ፡ ሥርዐትንና ፡ ፍርድን ፡ ያስተምር ፡
ዘንድ ፡ ልቡን ፡ አዘጋጅቶ ፡ ነበር ።

11 ፤ ንጉሡም ፡ አርጤክስስ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ ቃልና ፡ ለእስራኤል ፡ የኾነውን ፡ ሥርዐት ፡ ይጽፍ ፡ ለነበረው ፡
ለጸሓፊው ፡ ለካህኑ ፡ ለዕዝራ ፡ የሰጠው ፡ የደብዳቤው ፡ ግልባጭ ፡ ይህ ፡ ነው ።

12 ፤ ከንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ከአርጤክስስ ፡ ለሰማይ ፡ አምላክ ፡ ሕግ ፡ ጸሓፊ ፡ ለካህኑ ፡ ለዕዝራ ፥ ሙሉ ፡ ሰላም ፡ ይኹን ፤

13 ፤ በመንግሥቴ ፡ ውስጥ ፡ ካሉ ፡ ከእስራኤል ፡ ሕዝብ ፡ ከካህናቱና ፡ ከሌዋውያኑም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ይኼድ ፡
ዘንድ ፡ የሚወድ ፡ ኹሉ ፡ ከአንተ ፡ ጋራ ፡ እንዲኼድ ፡ አዝዣለኹ ።

14 ፤ በእጅኽ ፡ እንዳለችው ፡ እንደ ፡ አምላክኽ ፡ ሕግ ፡ ይሁዳንና ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ ትጐበኝ ፡ ዘንድ ፥

15 ፤ ንጉሡንና ፡ አማካሪዎቹም ፡ መኖሪያው ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ለኾነው ፡ ለእስራኤል ፡ አምላክ ፡ በፈቃዳቸው ፡ ያቀረቡትን ፡
ብርና ፡ ወርቅ ፥

16 ፤ በባቢሎንም ፡ አውራጃ ፡ ኹሉ ፡ የምታገኘውን ፡ ብርና ፡ ወርቅ ፡ ኹሉ ፥ ሕዝቡና ፡ ካህናቱም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ላለው ፡
ለአምላካቸው ፡ ቤት ፡ በፈቃዳቸው ፡ የሚያቀርቡትን ፡ ትወስድ ፡ ዘንድ ፡ በንጉሡና ፡ በሰባቱ ፡ አማካሪዎች ፡ ተልከኻልና ፤

17 ፤ ስለዚህ ፥ በዚህ ፡ ገንዘብ ፡ ወይፈኖችንና ፡ አውራ ፡ በጎችን ፥ ጠቦቶችንም ፥ የእኽላቸውንና ፡ የመጠጣቸውን ፡
ቍርባን ፡ ተግተኽ ፡ ግዛ ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ ባለው ፡ በአምላካችኹ ፡ ቤት ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ፡ አቅርባቸው ።

18 ፤ ከቀረውም ፡ ብርና ፡ ወርቅ ፡ አንተና ፡ ወንድሞችኽ ፡ ለማድረግ ፡ ደስ ፡ የሚያሠኛችኹን ፡ ነገር ፡ እንደ ፡
አምላካችኹ ፡ ፈቃድ ፡ አድርጉ ።

19 ፤ ስለአምላክኽም ፡ ቤት ፡ አገልግሎት ፡ የተሰጠኽን ፡ ዕቃ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ አምላክ ፡ ፊት ፡ አሳልፈኽ ፡ ስጥ ።

20 ፤ ከዚህም ፡ በላይ ፡ ለማውጣት ፡ የሚያስፈልግኽን ፡ ለአምላክኽ ፡ ቤት ፡ የሚያሻውን ፡ ነገር ፡ ከንጉሡ ፡ ቤተ ፡
መዛግብት ፡ አውጣ ።

21 ፤ እኔም ፡ ንጉሡ ፡ አርጤክስስ ፡ በወንዝ ፡ ማዶ ፡ ላሉት ፡ በጅሮንዶች ፡ ኹሉ ፡ ይህን ፡ ትእዛዝ ፡ ሰጥቻለኹ ። የሰማይ ፡
አምላክ ፡ ሕግ ፡ ጸሓፊ ፡ ካህኑ ፡ ዕዝራ ፡ ከእናንተ ፡ የሚፈልገውን ፡ ኹሉ ፡ አዘጋጁለት ፤

22 ፤ እስከ ፡ መቶ ፡ መክሊት ፡ ብርም ፡ ቢኾን ፥ እስከ ፡ መቶ ፡ የቈሬስ ፡ መስፈሪያ ፡ ስንዴ ፥ እስከ ፡ መቶም ፡ የባዶስ ፡
መስፈሪያ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፥ እስከ ፡ መቶም ፡ የባዶስ ፡ መስፈሪያ ፡ ዘይት ፡ ቢኾን ፥ ጨውም ፡ ያለልክ ፡ ቢኾን ፡ ስጡ ።

23 ፤ በንጉሡና ፡ በልጆቹ ፡ መንግሥት ፡ ላይ ፡ ቍጣ ፡ እንዳይኾን ፥ የሰማይ ፡ አምላክ ፡ ያዘዘው ፡ ኹሉ ፡ ለሰማይ ፡
አምላክ ፡ ቤት ፡ በሙሉ ፡ ይደረግ ።

24 ፤ ደግሞም ፡ በካህናቱና ፡ በሌዋውያን ፡ በመዘምራኑም ፡ በበረኛዎቹም ፡ በናታኒምም ፡ በዚህም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡
በሚሠሩ ፡ አገልጋዮች ፡ ላይ ፡ ግብርና ፡ ቀረጥ ፡ መጥንም ፡ እንዳይጣል ፡ ብለን ፡ እናስታውቃችኋለን ።

25 ፤ አንተም ፡ ዕዝራ ፥ በእጅኽ ፡ እንዳለው ፡ እንደ ፡ አምላክኽ ፡ ጥበብ ፡ መጠን ፡ በወንዝ ፡ ማዶ ፡ ባሉ ፡ ሕዝብ ፡ ኹሉ ፡
የአምላክኽን ፡ ሕግ ፡ በሚያውቁ ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፡ ይፈርዱ ፡ ዘንድ ፡ ዳኛዎችንና ፡ ፈራጆች ፡ አስነሣ ፤ የማያውቁትንም ፡
አስተምሯቸው ።

26 ፤ የአምላክኽንም ፡ሕግ ፥ የንጉሡንም ፡ ሕግ ፡ በማያደርግ ፡ ዅሉ ፡ ላይ ፡ ሞት ፡ ወይም ፡ ስደት ፡ ወይም ፡ ገንዘብን ፡ መወረስ ፡ ወይም ፡ ግዞት ፡ በፍጥነት ፡ ይፈረድበት ።

27 ፤ 28 ፤ በኢየሩሳሌም ፡ ያለውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ያሳምር ፡ ዘንድ ፡ እንደዚህ ፡ ያለውን ፡ ነገር ፡ በንጉሡ ፡ ልብ ፡ ያኖረ ፥ በንጉሡም ፡ በአማካሪዎቹም ፡ በንጉሡም ፡ ኀያላን ፡ አለቃዎች ፡ ዅሉ ፡ ፊት ፡ ምሕረቱን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ የላከ ፡ የአባቶቻችን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይባረክ ። እኔም ፡ በላዬ ፡ ባለችው ፡ በአምላኬ ፡ በእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ በረታኹ ፤ ከእኔም ፡ ጋራ ፡ እንዲወጡ ፡ ከእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ አለቃዎችን ፡ ሰበሰብኹ ።

## መጽሐፈ ፡ ዕዝራ ፥ ምዕራፍ ፡ 8 ።

ምዕራፍ ፡ 8 ።

1 ፤ በንጉሡ ፡ በአርጤክስስ ፡ መንግሥት ፡ ከእኔ ፡ ጋራ ፡ ከባቢሎን ፡ የወጡ ፡ የአባቶች ፡ ቤቶች ፡ አለቃዎች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፡ ትውልዳቸውም ፡ ይህ ፡ ነው ፤

2 ፤ ከፊንሐስ ፡ ልጆች ፡ ጌርሶን ፥ ከኢታምር ፡ ልጆች ፡ ዳንኤል ፥ ከዳዊት ፡ ልጆች ፡ ሐጡስ ፥ ከሴኬንያ ፡ ልጆች ፥

3 ፤ ከፋሮስ ፡ ልጆች ፡ ዘካርያስ ፥ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ መቶ ፡ ዐምሳ ፡ ወንዶች ፡ በትውልድ ፡ ተቈጠሩ ።

4 ፤ ከፋሐት ፡ ሞዐብ ፡ ልጆች ፡ የዘራእያ ፡ ልጅ ፡ ኤሊሆዔናይ ፥ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ ኹለት ፡ መቶ ፡ ወንዶች ።

5 ፤ ከሴኬንያ ፡ ልጆች ፡ የየሕዚኤል ፡ ልጅ ፥ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ወንዶች ።

6 ፤ ከዓዲን ፡ ልጆች ፡ የዮናታን ፡ ልጅ ፡ ዔቤድ ፥ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ ዐምሳ ፡ ወንዶች ።

7 ፤ ከዔላም ፡ ልጆች ፡ የጎቶልያ ፡ ልጅ ፡ የሻያ ፥ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ ሰባ ፡ ወንዶች ።

8 ፤ የሰፋጥያስ ፡ ልጆች ፡ የሚካኤል ፡ ልጅ ፡ ዝባድያ ፥ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ ሰማንያ ፡ ወንዶች ።

9 ፤ ከኢዮአብ ፡ ልጆች ፡ የይሒኤል ፡ ልጅ ፡ ዐብድዩ ፥ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ ኹለት ፡ መቶ ፡ ዐሥራ ፡ ስምንት ፡ ወንዶች ።

10 ፤ ከሰሎሚት ፡ ልጆች ፡ የዮሲፍያ ፡ ልጅ ፥ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ መቶ ፡ ስድሳ ፡ ወንዶች ።

11 ፤ ከቤባይ ፡ ልጆች ፡ የቤባይ ፡ ልጅ ፡ ዘካርያስ ፥ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ ኻያ ፡ ስምንት ፡ ወንዶች ።

12 ፤ ከዓዝጋድ ፡ ልጆች ፡ የሃቃጣን ፡ ልጅ ፡ ዮሐናን ፥ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ መቶ ፡ ዐሥር ፡ ወንዶች ።

13 ፤ ከኋለኛዎቹ ፡ ከአዶኒቃም ፡ ልጆች ፡ ስማቸው ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ኤሊፋላት ፥ ይዑኤል ፥ ሸማያ ፥ ከነርሱም ፡ ጋራ ፡ ስድሳ ፡ ወንዶች ።

14 ፤ ከበጉዋይ ፡ ልጆች ፡ ዑታይና ፡ ዘቡድ ፥ ከነርሱም ፡ ጋራ ፡ ሰባ ፡ ወንዶች ።

15 ፤ ወደ ፡ አህዋም ፡ ወደሚፈስ ፡ ወንዝ ፡ ሰበሰብኋቸው ፥ በዚያም ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ ሰፈርን ፤ ሕዝቡንና ፡ ካህናቱን ፡ ስቈጥራቸው ፡ በዚያ ፡ ከሌዊ ፡ ልጆች ፡ ማንንም ፡ አላገኘኹም ።

16 ፤ ወደ ፡ አለቃዎቹም ፡ ወደ ፡ አልዓዛር ፥ ወደ ፡ አርኤል ፥ ወደ ፡ ሸማያ ፥ ወደ ፡ ኤልናታን ፥ ወደ ፡ ያሪብ ፥ ወደ ፡ ኤልናታን ፥ ወደ ፡ ናታን ፥ ወደ ፡ ዘካርያስ ፥ ወደ ፡ ሜሱላም ፥ ደግሞም ፡ ወደ ፡ ዐዋቂዎቹ ፡ ወደ ፡ ዮያሪብና ፡ ወደ ፡ ኤልናታን ፡ ላክኹ ።

17 ፤ በካሲፍያ ፡ ስፍራ ፡ ወደነበረው ፡ ወደ ፡ አለቃው ፡ ወደ ፡ አዶ ፡ ላክኋቸው ፤ ለአምላካችን ፡ ቤት ፡ አገልጋዮችን ፡ ያመጡልን ፡ ዘንድ ፡ በካሲፍያ ፡ ስፍራ ፡ ለሚኖሩት ፡ ለአዶና ፡ ለወንድሞቹ ፡ ለናታኒም ፡ የሚነግሯቸውን ፡ በአፋቸው ፡ አደረግኹ ።

18 ፤ በላያችንም ፡ መልካም ፡ በኾነው ፡ በአምላካችን ፡ እጅ ፡ ከእስራኤል ፡ ልጅ ፡ ከሌዊ ፡ ልጅ ፡ ከሞሖሊ ፡ ልጆች ፡ ወገን ፡ የነበረውን ፡ አስተዋይ ፡ ሰው ፡ ሰራብያን ፥ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ ዐሥራ ፡ ስምንቱን ፡ ልጆቹንና ፡ ወንድሞቹን ፡ አመጡልን ።

19 ፤ ደግሞም ፡ ሐሸብያን ፡ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ ከሜራሪ ፡ ልጆች ፡ ወገን ፡ የነበረውን ፡ የሻያንና ፡ ኻያውን ፡ ወንድሞቹንና ፡ ልጆቻቸውን ።

20 ፤ ሌዋውያንንም ፡ እንዲያገለግሉ ፡ ዳዊትና ፡ አለቃዎቹ ፡ ከሰጧቸው ፡ ናታኒም ፡ ውስጥ ፡ ኹለት ፡ መቶ ፡ ኻያ ፡ ናታኒም ፡ አመጡ ፤ እነዚህም ፡ ኹሉ ፡ በስም ፡ በስማቸው ፡ ተጠሩ ።

21 ፤ በአምላካችን ፡ ፊት ፡ ራሳችንን ፡ እናዋርድ ፡ ዘንድ ፥ ከርሱም ፡ የቀናውን ፡ መንገድ ፡ ለእኛና ፡ ለልጆቻችን ፡ ለንብረታችንም ፡ ኹሉ ፡ እንለምን ፡ ዘንድ ፡ በዚያ ፡ በአህዋ ፡ ወንዝ ፡ አጠገብ ፡ ጾም ፡ ዐወጅኹ ።

22 ፤ ንጉሡንም ፦ የአምላካችን ፡ እጅ ፡ በሚሹት ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፡ ለመልካም ፡ ነው ፤ ኀይሉና ፡ ቍጣው ፡ ግን ፡ ርሱን ፡ በሚተዉ ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፡ ነው ፡ ብለን ፡ ተናግረን ፡ ነበርና ፥ በመንገድ ፡ ካለው ፡ ጠላት ፡ ያድኑን ፡ ዘንድ ፥ ጭፍራና ፡ ፈረሰኞዎች ፡ ከንጉሡ ፡ እለምን ፡ ዘንድ ፡ ዐፍሬ ፡ ነበርና ።

23 ፤ ስለዚህም ፡ ነገር ፡ ጾምን ፥ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ለመንን ፤ ርሱም ፡ ተለመነን ።

24 ፤ ከካህናቱም ፡ አለቃዎች ፡ ዐሥራ ፡ ኹለት ፡ ሰዎችን ፥ ሰራብያንና ፡ ሐሸቢያን ፡ ከነርሱም ፡ ጋራ ፡ ዐሥር ፡ ወንድሞቻቸውን ፡ ለየኹ ፤

25 ፤ ንጉሡና ፡ አማካሪዎቹ ፡ አለቃዎቹም ፡ በዚያም ፡ የተገኙት ፡ እስራኤል ፡ ኹሉ ፡ ያቀረቡትን ፡ ለአምላካችን ፡ ቤት ፡ የቀረበውን ፡ ብሩንና ፡ ወርቁን ፡ ዕቃውንም ፡ መዝኜ ፡ ሰጠኋቸው ።

26 ፤ ስድስት ፡ መቶ ፡ ዐምሳ ፡ መክሊት ፡ ብር ፥ አንድ ፡ መቶም ፡ መክሊት ፡ የብር ፡ ዕቃዎች ፥ አንድ ፡ መቶም ፡ መክሊት ፡ ወርቅ ፥

27 ፤ ኻያም ፡ ባለሺሕ ፡ ዳሪክ ፡ የወርቅ ፡ ጽዋዎች ፥ ኹለትም ፡ እንደ ፡ ወርቅ ፡ የከበሩ ፡ ከጥሩ ፡ ከሚያንጸባርቅ ፡ ናስ ፡ የተሠሩ ፡ ዕቃዎች ፡ መዝኜ ፡ በእጃቸው ፡ ሰጠኹ ።

28 ፤ እኔም ፦ እናንተ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ተቀድሳችኋል ፥ ዕቃዎቹም ፡ ቅዱስ ፡ ናቸው ፤ ብሩና ፡ ወርቁም ፡ ለአባቶቻችን ፡ አምላክ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በፈቃድ ፡ የቀረበ ፡ ነው ፤

29 ፤ በካህናትና ፡ በሌዋውያን ፡ አለቃዎች ፡ በእስራኤልም ፡ አባቶች ፡ ቤቶች ፡ አለቃዎች ፡ ፊት ፡ በኢየሩሳሌም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ጓዳዎች ፡ ውስጥ ፡ እስክትመዝኑ ፡ ድረስ ፡ ተግታችኹ ፡ ጠብቁ ፡ አልኋቸው ።

30 ፤ ካህናቱና ፡ ሌዋውያኑም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወደአምላካችን ፡ ቤት ፡ ይወስዱት ፡ ዘንድ ፡ ብሩንና ፡ ወርቁን ፡ ዕቃዎቹንም ፡ በሚዛን ፡ ተቀበሉ ።

31 ፤ በመዠመሪያውም ፡ ወር ፡ በዐሥራ ፡ ኹለተኛው ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ እንኼድ ፡ ዘንድ ፡ ከአህዋ ፡ ወንዝ ፡ ተነሣን ፡ የአምላካችንም ፡ እጅ ፡ በላያችን ፡ ነበረ ፥ በመንገድም ፡ ከጠላትና ፡ ከሚሸምቅ ፡ ሰው ፡ እጅ ፡ አዳነን ።

32 ፤ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ደረስን ፥ በዚያም ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ ተቀመጥን ።

33 ፤ በአራተኛውም ፡ ቀን ፡ ብሩና ፡ ወርቁ ፡ ዕቃዎቹም ፡ በአምላካችን ፡ ቤት ፡ በካህኑ ፡ በኦርዮ ፡ ልጅ ፡ በሜሪሞት ፡ እጅ ፡ ተመዘኑ ፤ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ የፊንሐስ ፡ ልጅ ፡ አልዓዛር ፡ ነበረ ፡ ከነርሱም ፡ ጋራ ፡ ሌዋውያን ፡ የኢያሱ ፡ ልጅ ፡ ዮዛባትና ፡ የቢንዊ ፡ ልጅ ፡ ኖዓድያ ፡ ነበሩ ።

34 ፤ ኹሉም ፡ በቍጥርና ፡ በሚዛን ፡ ተመዘነ ፤ ሚዛኑም ፡ ኹሉ ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ተጻፈ ።

35 ፤ ከምርኮም ፡ የወጡት ፡ ምርኮኞዎች ፡ ለእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ለሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ስለ ፡ እስራኤል ፡ ኹሉ ፡ ዐሥራ ፡ ኹለት ፡ ወይፈኖች ፥ ዘጠና ፡ ስድስትም ፡ አውራ ፡ በጎች ፥ ሰባ ፡ ሰባትም ፡ ጠቦቶች ፥ ለኀጢአት ፡ መሥዋዕት ፡ ዐሥራ ፡ ኹለት ፡ አውራ ፡ ፍየሎች ፡ አቀረቡ ። ይህ ፡ ኹሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የሚቃጠል ፡ መሥዋዕት ፡ ነበረ ።

36 ፤ የንጉሡንም ፡ ትእዛዝ ፡ በወንዙ ፡ ማዶ ፡ ላሉት ፡ ለንጉሡ ፡ ሹማምቶችና ፡ ገዢዎች ፡ ሰጡ ፤ እነርሱም ፡ ሕዝቡንና ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ አገዙ ።

መጽሐፈ ፡ ዕዝራ ፥ ምዕራፍ ፡ 9 ።

ምዕራፍ ፡ 9 ።

1 ፤ ይህም ፡ ከተፈጸመ ፡ በኋላ ፡ አለቃዎቹ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ቀርበው ፦ የእስራኤል ፡ ሕዝብ ፡ ካህናቱም ፡ ሌዋውያኑም ፡ እንደ ፡ ከነዓናውያን ፡ እንደ ፡ ኬጢያውያን ፡ እንደ ፡ ፌርዛውያን ፡ እንደ ፡ ኢያቡሳውያን ፡ እንደ ፡ አሞናውያን ፡ እንደ ፡

ሞዐባውያን ፡ እንደ ፡ ግብጻውያንና ፡ እንደ ፡ አሞራውያን ፡ ርኵሰት ፡ ያደርጋሉ ፡ እንጂ ፡ ከምድር ፡ አሕዛብ ፡ አልተለዩም ፤

2 ፤ ለራሳቸውና ፡ ለልጆቻቸውም ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻቸውን ፡ ወስደዋል ፥ የተቀደሰውንም ፡ ዘር ፡ ከምድር ፡ አሕዛብ ፡ ጋራ ፡ ደባልቀዋል ፤ አስቀድሞም ፡ አለቃዎቹና ፡ ሹማምቶቹ ፡ በዚህ ፡ መተላለፍ ፡ መገመሪያ ፡ ኾነዋል ፡ አሉኝ ።

3 ፤ ይህንም ፡ ነገር ፡ በሰማኹ ፡ ጊዜ ፡ ልብሴንና ፡ መጐናጸፊያዬን ፡ ቀደድኹ ፥ የራሴንና ፡ የጢሜንም ፡ ጠጕር ፡ ነጨኹ ፥ ደንግጬም ፡ ተቀመጥኹ ።

4 ፤ ስለምርኮኛዎቹም ፡ መተላለፍ ፡ የእስራኤልን ፡ አምላክ ፡ ቃል ፡ የሚፈሩ ፡ ኹሉ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ተሰበሰቡ ፤ እኔም ፡ እስከሠርክ ፡ መሥዋዕት ፡ ድረስ ፡ ደንግጬ ፡ ተቀመጥኹ ።

5 ፤ በሠርክም ፡ መሥዋዕት ፡ ጊዜ ፡ ልብሴና ፡ መጐናጸፊያዬ ፡ እንደ ፡ ተቀደደ ፡ ኾኖ ፡ ከመዋረዴ ፡ ተነሣኹ ፤ በጕልበቴም ፡ ተንበርክኬ ፡ ወደ ፡ አምላኬ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እጄን ፡ ዘረጋኹ ።

6 ፤ እንዲህም ፡ አልኹ ፦ አምላኬ ፡ ሆይ ፥ ኀጢአታችን ፡ በራሳችን ፡ ላይ ፡ በዝቷልና ፥ በደላችንም ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብሏልና ፥ አምላኬ ፡ ሆይ ፥ ፊቴን ፡ ወዳንተ ፡ አነሣ ፡ ዘንድ ፡ ዐፍራለኹ ፥ እፈራማለኹ ።

7 ፤ ከአባቶቻችን ፡ ዘመን ፡ ዠምረን ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ እጅግ ፡ በድለናል ፤ ዛሬም ፡ እንደ ኾነው ፡ ስለ ፡ ኀጢአታችን ፡ እኛና ፡ ንጉሦቻችን ፡ ካህናታችንም ፡ ለሰይፍና ፡ ለምርኮ ፡ ለብዝበዛና ፡ ለዕፍረት ፡ በምድር ፡ ነገሥታት ፡ እጅ ፡ ተጣልን ።

8 ፤ አኹንም ፡ ቅሬታ ፡ ይተውልን ፡ ዘንድ ፥ በተቀደሰውም ፡ ስፍራው ፡ ችንካርን ፡ ይሰጠን ፡ ዘንድ ፥ አምላካችንም ፡ ዐይናችንን ፡ ያበራ ፡ ዘንድ ፥ በባርነትም ፡ ሳለን ፡ ጥቂት ፡ የሕይወት ፡ መታደስን ፡ ይሰጠን ፡ ዘንድ ፡ ለጥቂት ፡ ጊዜ ፡ ከአምላካችን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ሞገስ ፡ ተሰጥቶናል ።

9 ፤ ባሪያዎች ፡ ነንና ፥ አምላካችን ፡ ግን ፡ በባርነታችን ፡ አልተወንም ፤ የሕይወት ፡ መታደስን ፡ ይሰጠን ፡ ዘንድ ፥ የአምላካችንንም ፡ ቤት ፡ እንሠራ ፡ ዘንድ ፥ የተፈታውንም ፡ እንጠግን ፡ ዘንድ ፥ በይሁዳና ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ ቅጥር ፡ ይደረግልን ፡ ዘንድ ፡ በፋርስ ፡ ነገሥታት ፡ ፊት ፡ ምሕረቱን ፡ ሰጠን ።

10 ፤ 11 ፤ 12 ፤ አኹንስ ፡ አምላካችን ፡ ሆይ ፦ ትወርሷት ፡ ዘንድ ፡ የምትገቡባት ፡ ምድር ፡ በምድር ፡ አሕዛብ ፡ ርኵሰት ፡ ረክሳለች ፥ ከዳር ፡ እስከ ፡ ዳርም ፡ ድረስ ፡ ከርኵሰታቸው ፡ ከጸያፍ ፡ ሥራቸውም ፡ ተሞልታለች ፤ አኹንም ፡ ትበረቱ ፡ ዘንድ ፥ የምድሩንም ፡ ፍሬ ፡ ትበሉ ፡ ዘንድ ፥ ለዘለዓለም ፡ ለልጆቻችኹ ፡ ታወርሷት ፡ ዘንድ ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻችኹን ፡ ለልጆቻቸው ፡ አትስጡ ፥ ሴቶች ፡ ልጆቻቸውንም ፡ ለልጆቻችኹ ፡ አትውሰዱ ፥ ሰላማቸውንና ፡ ደኅንነታቸውንም ፡ ለዘለዓለም ፡ አትሹ ፡ ብለኽ ፡ በባሪያዎችኽ ፡ በነቢያት ፡ ያዘዝኸውን ፡ ትእዛዝ ፡ ትተናልና ፥ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ምን ፡ እንላለን ፧

13 ፤ ስለ ፡ ክፉ ፡ ሥራችንና ፡ ስለ ፡ ታላቁ ፡ በደላችን ፡ ካገኘን ፡ ነገር ፡ ኹሉ ፡ በኋላ ፥ አንተ ፡ አምላካችን ፡ እንደ ፡ ኀጢአታችን ፡ ብዛት ፡ አልቀሠፍኸንም ፥ ነገር ፡ ግን ፥ ቅሬታን ፡ ሰጠኸን ።

14 ፤ በእውኑ ፡ ተመልሰን ፡ ትእዛዝኽን ፡ እናፈርስ ፡ ዘንድ ፥ ርኩስ ፡ ሥራን ፡ ከሚሠሩ ፡ ከነዚህም ፡ አሕዛብ ፡ ጋራ ፡ እንገባ ፡ ዘንድ ፡ ይገባናልን ፧ አንተስ ፡ ቅሬታ ፡ የሌለንና ፡ የማናመልጥ ፡ እስክንኾን ፡ ድረስ ፡ እንድታጠፋን ፡ አትቈጣንም ፧

15 ፤ አቤቱ ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፥ አንተ ፡ ጻድቅ ፡ ነኽ ፤ ዛሬም ፡ እንደ ኾነው ፡ እኛ ፡ አምልጠን ፡ ቀርተናል ፤ እንሆ ፥ በፊትኽ ፡ በበደላችን ፡ አለን ፤ ስለዚህ ፥ በፊትኽ ፡ ሊቆም ፡ የሚችል ፡ የለም ።

## መጽሐፈ ፡ ዕዝራ ፥ ምዕራፍ ፡ 10 ።

ምዕራፍ ፡ 10 ።

1 ፤ ዕዝራም ፡ እያለቀሰና ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ፊት ፡ እየወደቀ ፡ በጸለየና ፡ በተናዘዘ ፡ ጊዜ ፡ ከእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ የወንድና ፡ የሴት ፡ የሕፃናትም ፡ እጅግ ፡ ታላቅ ፡ ጉባኤ ፡ ወደ ፡ ርሱ ፡ ተሰበሰበ ፤ ሕዝቡም ፡ እጅግ ፡ አለቀሱ ።

2 ፤ ከዔላም ፡ ልጆች ፡ ወገን ፡ የነበረም ፡ የይሒኤል ፡ ልጅ ፡ ሴኬንያ ፡ ዕዝራን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረው ፦ አምላካችንን ፡ በድለናል ፤ የምድርን ፡ አሕዛብ ፡ እንግዳዎች ፡ ሴቶችን ፡ አግብተናል ፤ አኹን ፡ ግን ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ገና ፡ ለእስራኤል ፡ ተስፋ ፡ አለ ።

፬ ቃልየ ፡ ኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡ጸራኅኩ ።
ወሰምዐኒ ፡ እምደብረ ፡ መቅደሱ ።
፭ አንሰ ፡ ሰከብኩ ፡ ወኖምኩ ።
ወተንሣእኩ ፡ እስመ ፡ እግዚአብሔር አንሥአኒ ።
፮ ኢይፈርህ ፡ እምአእላፍ ፡ አሕዛብ ።
እለ ፡ ዐገቱኒ ፡ ወቆሙ ፡ ላዕሌየ ።
፯ ተንሥኢ ፡ እግዚኦ ፡ አምላኪየ ፡ ወአድኅነኒ ።
እስመ ፡ አንተ ፡ ቀሠፍኮሙ ፡ ለኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይፃረሩኒ ፡ በከንቱ ።
ስነኒሆሙ ፡ ለኃጥአን ፡ ሰበርከ ።
፰ ዘእግዚአብሔር ፡ አድኅኖ፡ ላዕለ፡ሕዝብከ፡ወበረከትከ።

መዝሙር ፡ ፬ ።

በ እ ን ተ ፡ ማ ኒ ።

፩ ሶበ ፡ ጸዋዕክዎ ፡ ለእግዚአብሔር ሰምዐኒ ፡ ጽድቅየ ።
ወእምንዳቤየ ፡ አርሐበ ፡ ሊተ ።
ተሣሃለኒ ፡ ወስምዐኒ ፡ ጸሎትየ ።
፪ ደቂቀ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ፡ እስከ ፡ ማእዜኑ ፡ ታከብዱ ልበክሙ ።
ለምንት ፡ ታፈቅሩ ፡ ከንቶ ፡ ወተኀሡ ፡ ሐሰተ ።
፫ አእምሩ ፡ ከመ ፡ ተሰብሐ ፡ እግዚአብሔር ብጻድቁ ።
እግዚአብሔር ፡ ይሰምዐኒ ፡ ሶበ፡ጸራኅኩ ፡ ኀቤሁ ።
፬ ተምዑ ፡ ወኢተአብሱ ።
ወዘትሔልዩ ፡ በልብክሙ ፡ ውስተ ፡ ምስካቢክሙ ፡ ይትዐወቅሙ ።
፭ ሡዑ፡መሥዋዕተ፡ጽድቅ፡ወተወከሉ፡ በእግዚአብሔር።
፮ ብዙኃን ፡ እለ ፡ ይቤሉ ፡ መኑ ፡ ያርእየነ ፡ ሠናይቶ ።
ተዐውቀ ፡ በላዕሌነ ፡ ብርሃነ ፡ ገጽከ ፡ እግዚኦ ።
፯ ወወደይከ ፡ ትፍሥሕተ ፡ ውስተ ፡ ልብነ ።
እምፍሬ ፡ ሥርናይ ፡ ወወይን ፡ ወቅብዕ ፡ በዝኀ ።
በሰላም ፡ ቦቱ ፡ እሰክብ ፡ ወእነውም ።
፰ እስመ፡አንተ፡ እግዚኦ፡ በተስፋ፡ ባሕቲትከ፡ አኅደርከኒ።

መዝሙር ፡ ፭ ።

ትንቢት ፡ በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ ቃልየ ፡ አጽምዕ ፡ እግዚኦ ።
ወለቡ ፡ ጽራኅየ ።
፪ ወአጽምዐኒ ፡ ቃለ ፡ ስእለትየ ።
ንጉሥየኒ ፡ ወአምላኪየኒ ።
እስመ ፡ ኀቤከ ፡ እጼሊ ፡ እግዚኦ ።
፫ በጽባሕ ፡ ስምዐኒ ፡ ቃልየ ።
በጽባሕ ፡ እቀውም ፡ ቅድሜከ ፡ ወአስተርኢ ፡ ለከ ።
፬ እስመ ፡ ኢኮንከ ፡ አምላከ ፡ ዘዐመፃ ፡ ያፈቅር ።
ወኢየኀድሩ ፡ እኩያን ፡ ምስሌከ ።
፭ ወኢይነብሩ ፡ ዐማፅያን ፡ ቅድመ ፡ አዕይንቲከ ።
ጸላእከ ፡ እግዚኦ ፡ ኵሎሙ ፡ ገበርተ ፡ ዐመፃ ።
፮ ወትገድፎሙ ፡ ለኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይነቡ ፡ ሐሰተ ።
ብእሴ ፡ ደም ፡ ወጕሕላዌ ፡ ያስቆርር፡ እግዚአብሔር ።
፯ ወአንሰ ፡ በብዝኀ ፡ ምሕረትከ ፡ እበውእ ፡ ቤተከ ።
ወእሰግድ ፡ ውስተ ፡ ጽርሐ ፡ መቅደስከ ፡ በፈሪሆትከ ።
፰ እግዚኦ ፡ ምርሐኒ ፡ በጽድቅከ ።
ወበእንተ ፡ ጸላእትየ ፡ አርትዕ ፡ ፍኖትየ ፡ ቅድሜከ ።
፱ እስመ ፡ አልቦ ፡ ጽድቅ ፡ ውስተ ፡ አፉሆሙ ።
ልቦሙኒ ፡ ከንቱ ።
ከመ ፡ መቃብር ፡ ክሡት ፡ ጐራዒቶሙ ።
ወጸልሐዉ ፡ በልሳናቲሆሙ ።
፲ ኰንኖሙ ፡ እግዚኦ ፡ ወይደቁ ፡ በውዲቶሙ ።
ወበከመ ፡ ብዝኀ ፡ ሕብሎሙ ፡ ስድዶሙ ።
እስመ ፡ አምረሩከ ፡ እግዚኦ ።



በቃሌ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር፡ እጮኻለሁ ፡ ፬
እሱም ፡ ከተቀደሰው ፡ ተራራው ፡ ይሰማኛል ።
እኔ ፡ ተኛሁ ፡ አንቀላፋሁም ፤ ፭
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ደግፎኛልና ፡ ነቃሁ ።
ከሚከቡኝም ፡ የሕዝብ ፡ ብዛት ፡ የተነሳ ፡ አልፈራም ። ፮
አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ ሆይ ፡ ተነሥ ፡ አድነኝም ፤ ፯
አንተ ፡ የጠላቶቼን ፡ መንጋጋ ፡ መትተሃልና ፡
የከፉዎችንም ፡ ጥርስ ፡ ሰብረሃልና ።
እንግዲህ ፡ ማዳን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ነው ፡ ፰
በረከትህም ፡ በሕዝብህ ፡ ላይ ፡ ነው ።

መዝሙር ፡ ፬ ።
ስ ለ ማ ኒ ።

የሰውነት ፡ አምላክ ፡ እሱ፡በጠራሁት፡ጊዜ፡መለሰልኝ ፡ ፩
በጭንቀቴም ፡ ጊዜ ፡ ደረሰልኝ ፡
ይቅር ፡ አለኝ ፡ ጸሎቴንም ፡ ሰማ ።
እናንት ፡ የሰው ፡ ልጆች፡ እስከ፡ መቼ ፡ ድረስ፡ ልባችሁን ፪
ታከብዳላችሁ ፤?
ከንቱ፡ ነገርንስ ፡ ስለምን ፡ ትወዳላችሁ ? ሐሰትንስ ፡
ለምን ፡ ትናገራላችሁ ።?
እግዚአብሔር ፡ በጻድቁ ፡ እንደ ፡ ተገለጠ ፡ እወቁ ፤ ፫
እግዚአብሔር ፡ ወደ፡እርሱ፡በተጣራሁ፡ጊዜ፡ይሰማኛል።
ተናገሩ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ሰውን ፡ አትበድሉ ፤ ፬
በመኝታችሁ፡ላይ ፡ ሳላችሁ ፡ በልባችሁ ፡ አስቡ፤በማስተዋልም፡ሁኑ ።
የጽድቅን፡ መሥዋዕት ፡ ሠዉ ፡ባእግዚአብሔር ታመኑ ። ፭
በጎውን ፡ ነገር ፡ ማን፡ያሳየናል ? የሚሉ፡ ብዙ፡ ናቸውና፤ ፮
አቤቱ ፡ የፊትህ ፡ ብርሃን ፡ በላያችን ፡ በራ ።
በልቤም ፡ ውስጥ ፡ ደስታን ፡ መላህ ፤ ፯
ከስንዴ፡ ፍሬና፡ ከወይን ፡ ዘለላ ፡ ከዘይትም ፡ ይልቅ፡ በዛ ።
በሰላም ፡ እተኛለሁ ፡ አንቀላፋለሁም ፤ ፰
አቤቱ ፡ አንተ ፡ ብቻህን ፡ በእምነት ፡ አሳድረኸኛልና ።

መዝሙር ፡ ፭ ።
ትንቢት ፡ ስለትሩፋን ።

አቤቱ ፡ቃሌን ፡ አድምጥ ፡ ፩
ጩኸቴንም ፡ አስተውል ።
የልመናዬን ፡ ቃል ፡ ስማ ፡ ፪
ንጉሤና ፡ አምላኬ ፡ ሆይ ፡
አቤቱ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ እጸልያለሁና ።
በማለዳ ፡ ድምፄን ፡ ትሰማለህ ፤ ፫
ማለዳ ፡ በፊትህ ፡ እቆማለሁ ፡ እጠብቃለሁም ።
አንተ ፡ በደልን ፡ የማትወድ ፡ አምላክ፡ ነህና ፤ ፬
ተንኰለኞች ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ አያድሩም ።
አመፀኞችም ፡ በፊትህ ፡ አይኖሩም ፤ ፭
ክፉ ፡ አድራጊዎችን ፡ ሁሉ ፡ ጠላህ ።
ሐሰት ፡ የሚናገሩትን ፡ ታጠፋቸዋለህ ፤ ፮
ነፍሰ፡ገዳዩንና፡አታላይ፡ወንበዴውን፡ሰው፡ እግዚአብሔር፡ይጸየፈዋል ።
እኔ፡ ግን፡ በይቅርታህ፡ ብዛት ፡ ወደ ፡ ቤትህ ፡ እገባለሁ ፤ ፯
አንተን፡ በመፍራት፡ በቅድስናህ ፡ መቅደስ ፡ እሰግዳለሁ ።
አቤቱ ፡ ስለ ፡ ጠላቶቼ ፡ በጽድቅህ ፡ ምራኝ ፤ ፰
መንገዴን ፡ በፊትህ፡ አቅና ።
በአፋቸው ፡ እውነት ፡ የለምና ፤ ፱
ልባቸውም ፡ ከንቱ ፡ ነው ፤
ጕረሮቸው ፡ የተከፈተ ፡ መቃብር ፡ ነው ፤
በአንደበታቸው ፡ ይሸነግላሉ ።
አቤቱ ፡ ፍረድባቸው ፡ በክፉ ፡ ምክራቸውም ፡ ይውደቁ ፲
ስለ ፡ ክፋታቸውም ፡ ብዛት ፡ አሳዳቸው ፡
እነርሱ ፡ ዐምፀውብሃልና ።

፲፩ ወይትፌሥሑ ፡ ብከ ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይትዌከሉከ ።
ለዓለም ፡ ይትሐሠዩ ፡ ወተሐድር ፡ ላዕሌሆሙ ።
ወይትሜክሁ ፡ ብከ ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ ያፈቅሩ ፡ ስመከ።
፲፪ እስመ ፡ አንተ ፡ ትባርኮ ፡ ለጻድቅ ።
እግዚኦ ፡ ከመ ፡ ወልታ ፡ ሥሙር ፡ ከለልከነ ።

መዝሙር ፡ ፮ ።

ዘርእሱ ፡ ወበአንተ ፡ አብሶቱ ፡ ምስለ ፡ ቤርሳቤሕ ።

፩ እግዚኦ ፡ በመዓትከ ፡ ኢትቅሥፈኒ ።
ወበመቅሠፍትከ ፡ ኢትገሥጸኒ ።
፪ ተሣሀለኒ ፡ እግዚኦ ፡ እስመ ፡ ድዉይ ፡ አነ ።
ወፈውሰኒ ፡ እስመ ፡ ተሀውከ ፡ አዕፅምትየ ።
፫ ነፍስየኒ ፡ ተሀውከት ፡ ፈድፋደ ።
ወአንተኒ ፡ እግዚኦ ፡ እስከ ፡ ማእዜኑ ።
፬ ተመየጥ ፡ እግዚኦ ፡ ወባልሃ ፡ ለነፍስየ ።
ወአድኅነኒ ፡ በእንተ ፡ ምሕረትከ ።
፭ እስመ ፡ አልቦ ፡ በውስተ ፡ ሞት ፡ ዘይዜክረከ ።
ወበሲኦልኒ ፡ መኑ ፡ የአምነከ ።
፮ ሠራሕኩ ፡ በምንዳቤየ ።
ወአሐፅብ ፡ ኵሎ ፡ ሌሊተ ፡ ዐራትየ ።
ወበአንብዕየ ፡ አርሐስኩ ፡ ምስካብየ ።
፯ ወተሀውከት ፡ እመዓት ፡ ዐይንየ ።
ወበለይኩ ፡ በኀበ ፡ ኵሎሙ ፡ ጸላእትየ ።
፰ ረሐቁ ፡ እምኔየ ፡ ኵልክሙ ፡ ገበርተ ፡ ዐመፃ ።
እስመ ፡ ሰምዐኒ ፡እግዚአብሔር፡ ቃለ ፡ ብካይየ ።
፱ ወሰምዐኒ ፡ እግዚአብሔር ፡ ስእለትየ ።
ወተወክፈ ፡እግዚአብሔር፡ ጸሎትየ ።
፲ ለይትኀፈሩ ፡ ወይኅሰሩ ፡ ኵሎሙ ፡ ጸላእትየ ።
ለይግብኡ፡ድኅሬሆሙ፡ወይትኀፈሩ፡ፈድፋደ፡ ፍጡነ ።

መዝሙር ፡ ፯ ።

በእንተ ፡ ርእሱ ፡ ወበእንተ ፡ አኪጦፌል ።

፩ እግዚኦ ፡አምላኪየ ፡ ብከ ፡ ተወከልኩ ፡ ኢትግድፈኒ ።
ወአድኅነኒ ፡ እምኵሎሙ ፡ እለ ፡ ሮዱኒ ፡ ወባልሀኒ ።
፪ ከመ ፡ ኢይምሥጥዋ ፡ ከመ ፡ አንበሳ ፡ ለነፍስየ ።
እንዘ ፡ አልቦ ፡ ዘያድኅን ፡ ወዘይባልሀ ።
፫ እግዚኦ ፡ አምላኪየ ፡ እመሰ ፡ ከመዝ ፡ ገበርኩ ።
ወእመኒቦ ፡ ዐመፃ ፡ ውስተ ፡ እደውየ ።
፬ ወእመኒ ፡ ፈደይክዎሙ ፡ ለእለ ፡ ይፈድዩኒ ፡ እኩየ ።
ለየውድቁኒ ፡ ጸላእትየ ፡ ዕራቅየ ።
፭ ወይዴግና ፡ ፀራዊ ፡ ለነፍስየ ፡ ወይርከባ ።
ወይኪዳ ፡ ውስተ ፡ ምድር ፡ ለሕይወትየ ።
ወያኅስሮ ፡ ውስተ ፡ መሬት ፡ ለክብርየ ።
፮ ተንሥእ ፡ እግዚኦ ፡ በመዓትከ ።
ወተለዐል ፡ መልዕልቶሙ ፡ ለጸላእትየ ።
ተንሥእ ፡ እግዚኦ ፡ አምላኪየ ፡ በሥርዐት ፡ ዘአዘዝከ።
፯ ወማኅበረ ፡ አሕዛብ ፡ የዐውደከ ።
ወበእንተዝ ፡ ተመየጥ ፡ ውስተ ፡ አርያም ።
፰ እግዚአብሔር ፡ይኬንኖሙ ፡ ለአሕዛብ ።
ፍታሕ ፡ ሊተ ፡ እግዚኦ ፡ አምላኪየ ፡ በከመ ፡ ጽድቅየ
ወይኩነኒ ፡ በከመ ፡ የዋሀትየ ።
፱ የኀልቅ ፡ እከዮሙ ፡ ለኃጥኣን ።
ወታረትዖሙ ፡ ለጻድቃን ።
ይፈትን ፡ ልበ ፡ ወኵልያተ ፡ እግዚአብሔር ።
፲ አማን ፡ ይረድአኒ ፡እግዚአብሔር ።
ዘያድኅኖሙ ፡ ለርቱዓነ ፡ ልብ ።
፲፩ እግዚአብሔር ፡መኰንን ፡ ጽድቅ ።
ኀያል ፡ ወመስተዐግሥ ።
ወኢያመጽእ ፡ መንሱተ ፡ ኵሎ ፡ አሚረ ።



በአንተ ፡ የሚታመኑት ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ ለዘላለሙ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፡ ፲፩
አንተ፡ሰንም፡ ትጠብቃለህ ፤
ስምህንም ፡ የሚወዱ ፡ ሁሉ ፡ በአንተ ፡ ይመካሉ ።
አንተ ፡ ጻድቁን ፡ ትባርከዋለህና ፤ ፲፪
አቤቱ ፡ እንደ ፡ ጋሻ ፡ በሞገስ ፡ ከለልኸን ።

መዝሙር ፡ ፮ ።

ከቤርሳቤሕ ፡ ጋር ፡ ስለመበደሉ ።

አቤቱ ፡ በቍጣህ ፡ አትቅሠፈኝ ፡ ፩
በመዓትህም ፡ አትገሥጸኝ ።
ድውይ ፡ ነኝና ፡ አቤቱ ፡ ማረኝ ፤ ፪
አጥንቶቼ ፡ ታውከዋልና ፡ ፈውሰኝ ።
ነፍሴም ፡ እጅግ ፡ ታወከች ፤ ፫
አንተም ፡ አቤቱ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ ነው ?
አቤቱ ፡ ተመለስ ፡ ነፍሴንም ፡ አድናት ፡ ፬
ስለ ፡ ቸርነትህም ፡ አድነኝ ።
በሞት ፡ የሚያስብህ ፡ የለምና ፡ ፭
በሲኦልም ፡ የሚያመሰግንህ ፡ ማን ፡ ነው ?
ከጭንቀቴ ፡ የተነሣ ፡ ደከሚያለሁ ፤ ፮
ሌሊቱን ፡ ሁሉ ፡ በዕንባዬ ፡ አልጋዬን ፡ አጥባለሁ ፡
መኝታዬንም ፡ አርሳለሁ ።
ዓይኔ ፡ ከመረር ፡ ዕንባ ፡ የተነሣ ፡ ታወከች ፤ ፯
በጠላቶቼ ፡ ዘንድ ፡ እንደአረጀሁ ፡ ተቈጠርሁ ።
እንግዴህስ ፡ ዓመፃን ፡ የምታደርጉ ፡ ሁሉ ፡ ከእኔ፡ ራቁ፤ ፰
እግዚአብሔር የልቅሶዬን፡ ቃል ፡ ሰምቶአልና ።
እግዚአብሔር፡ ልመናዬን ፡ ሰማ ፤ ፱
እግዚአብሔር፡ ጸሎቴን ፡ ተቀበለ ።
ጠላቶቼ ፡ ሁሉ፡ይፈሩ ፡ እጅግም ፡ ይጐስቍሉ ፤ ፲
አፍረውና ፡ ተዋርደውም ፡ ወደ ፡ ኋላቸው፡ ይመለሱ ።

መዝሙር ፡ ፯ ።

ስለራሱና ፡ ስለአኪጦፌል ።

አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ በአንተ ፡ እታመናለሁና ፡ ፩
ከሚያሳድዱኝ ፡ ሁሉ ፡ አድነኝ ፡ አውጣኝም ።
የሚያድንና ፡ የሚታደግ ፡ ካልኖረ ፡ ነፍሴን ፡ ፪
ነጥቀው ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ይሰብሩዋታልና ።
አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ እንዲህስ ፡ ካደረግሁ ፡ ፫
ዓመፃም ፡ በእጄ ፡ ቢኖር ።
ክፉ ፡ ላደረጉብኝም ፡ ክፉን ፡ መልሼላቸው ፡ ብሆን ፡ ፬
ጠላቴንም ፡ በከንቱ ፡ ገፍቼው ፡ ብሆን ።
ጠላት ፡ ነፍሴን ፡ ይከታተላት ፡ ፈልጎም ፡ ያግኛት ፡ ፭
ሕይወቴንም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ይርገጣት ፡
ክብሬንም ፡ በትቢያ ፡ ላይ ፡ ያዋርዳት ።
አቤቱ ፡ በመዓትህ ፡ ተነሥ ፡ ፮
በጠላቶቼም ፡ ላይ ፡ በቍጣ ፡ ተነሣባቸው ፤
አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ ባዘዝኸው ፡ ትእዛዝ ፡ ንቃ ።
የአሕዛብም ፡ ጉባኤ ፡ ይከብሃል ፡ ፯
በእነርሱም ፡ ላይ ፡ ወደ ፡ ከፍታ ፡ ተመለስ ።
እግዚአብሔር ፡ በአሕዛብ ፡ ይፈርዳል ፤ ፰
አቤቱ ፡ እንደ ፡ ጽድቁ ፡ ፍረድልኝ ፡
እንደ ፡ የዋህነቴም ፡ ይሁንልኝ ።
የኃጥአን ፡ ክፋት ፡ ይጥፋ ፡ ፱
ጻድቅን ፡ ግን ፡ አቅና ፤
እግዚአብሔር ልብንና ፡ ኵላሊትን ፡ ይመረምራል ።
ልበ ፡ ቅኖችን ፡ የሚያድናቸው ፡ እሱ ፤ ፲
እግዚአብሔር ፡ የጽድቅ ፡ ጋሻዬ ፡ ነው ።
እግዚአብሔር ፡ የእውነት ፡ ዳኛ ፡ ነው ፡ ፲፩
ኃይለኛም ፡ ታጋሽም ፡ ነው ፤
ሁል ፡ ጊዜም ፡ አይቆጣም ።

፲፪ እመሰ ፡ ኢተመየጥክሙ ፡ ሰይፎ ፡ ይመልኅ ።
ቀስቶኒ ፡ ወተረ ፡ ወአስተዳለወ ።
፲፫ ወአስተዳለወ ፡ ቦቱ ፡ ሕምዘ ፡ ዘይቀትል ።
ወአሕፃሁኒ ፡ እለ ፡ ይነዱ ፡ ገብረ ።
፲፬ ናሁ ፡ ሐመ ፡ ፀማዒ ፡ በፀመፃሁ ።
ፀንሰ ፡ በጻዕር ፡ ወወለደ ፡ ኃጢአተ ።
፲፭ ግበ ፡ ከረየ ፡ ወደጎየ ።
ወይወድቅ ፡ ውስተ ፡ ግብ ፡ ዘገብረ ።
፲፮ ወይገብእ ፡ ፃማሁ ፡ ዲበ ፡ ርእሱ ።
ወትወርድ ፡ ፀመፃሁ ፡ ዲበ ፡ ድማሁ ።
፲፯ እገኒ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በከመ ፡ ጽድቁ ።
ወእዜምር ፡ ለስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ልዑል ።

መዝሙር ፡ ፰ ።

ትንቢት ፡ በእንተ ፡ ክርስቶስ ።

፩ እግዚኦ ፡ እግዚእነ፡ጥቀ፡ተሰብሐ፡ስምከ፡በኵሉ፡ ምድር ።
እስመ፡ተለዐለ፡ዕበየ፡ስብሐቲከ፡ መልዕልተ፡ ሰማያት ።
፪ እምአፈ ፡ ደቂቅ ፡ ወሕፃናት ፡ አስተዳሎከ ፡ ስብሐተ ።
በእንተ ፡ ጸላዒ ።
ከመ ፡ ትንሥቶ ፡ ለጸላኢ ፡ ወለገፋዒ ።
፫ እስመ ፡ ንሬኢ ፡ ሰማያተ ፡ ግብረ ፡ አጻብዒከ ።
ወርኀ ፡ ወከዋክብተ ፡ ዘለሊከ ፡ ሣረርከ ።
፬ ምንትኑ ፡ ውእቱ ፡ ሰብእ ፡ ከመ ፡ ትዝክሮ ።
ወምንትኑ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ፡ ከመ ፡ ተሐውጾ ።
፭ ሐቀ ፡ አሕፀፅኮ ፡ እመላእክቲከ ።
ክብረ ፡ ወስብሐተ ፡ ከለልኮ ።
፮ ወሤምኮ ፡ ውስተ ፡ ኵሉ ፡ ግብረ ፡ እደዊከ ።
ወኵሎ ፡ አግረርከ ፡ ሎቱ ፡ ታሕተ ፡ እገሪሁ ።
፯ አባግዐኒ ፡ ወኵሎ ፡ አልሕምተ ።
ወዓዴ ፡ እንስሳ ፡ ዘገዳም ።
፰ አዕዋፈ ፡ ሰማይኒ ፡ ወዓሣተ ፡ ባሕር ።
ወዘኒ ፡ የሐውር ፡ ውስተ ፡ ፍኖተ ፡ ባሕር ።
፱ እግዚኦ፡እግዚእነ፡ጥቀ፡ተሰብሐ፡ስምከ፡በኵሉ፡ ምድር ።

መዝሙር ፡ ፱ ።

በእንተ ፡ ርእሱ ፡ ወበእንተ ፡ ገፋዒ ፡ ወተገፋዒ ።

፩ እገኒ ፡ ለከ ፡ እግዚኦ ፡ በኵሉ ፡ ልብየ ።
ወእነግር ፡ ኵሎ ፡ ስብሐቲከ ።
፪ እትፌሣሕ ፡ ወእትሐሠይ ፡ ብከ ።
ወእዜምር ፡ ለስምከ ፡ ልዑል ።
፫ ሶበ ፡ ገብኡ ፡ ጸላእትየ ፡ ድኅሬሆሙ ።
ይደወዩ ፡ ወይትሀጐሉ ፡ እምቅድመ ፡ ገጽከ ።
፬ እስመ ፡ ገበርከ ፡ ሊተ ፡ ፍትሕየ ፡ ወበቀልየ ።
ወነበርከ ፡ ዲበ ፡ መንበርከ ፡ መኰንን ፡ ጽድቅ ።
፭ ገሠጽኮሙ ፡ ለአሕዛብ ፡ ወተሀጕሉ ፡ ረሲዓን ።
ወደምሰስከ ፡ ስሞሙ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ።
፮ ፀርሰ ፡ ተገምሩ ፡ በኲናት ፡ ለዝሉፉ ።
ወአህጉሪሆሙኒ ፡ ነሠትከ ።
ወትስዕር ፡ ዝክሮሙ ፡ ኀበ ፡ ኀቡረ ።
፯ እግዚአብሔርሰ ፡ ይነብር ፡ ለዓለም ።
ወአስተዳለወ ፡ መንበሮ ፡ ለኰንኖ ።
፰ ወውእቱ ፡ ይኴንና ፡ ለዓለም ፡ በጽድቅ ።
ወይኴንኖሙ ፡ ለአሕዛብ ፡ በርትዕ ።
፱ ወኮኖሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ ምስካዮሙ ፡ ለነዳያን ።
ወረዳኢሆሙ ፡ ውእቱ ፡ በጊዜ ፡ ምንዳቤሆሙ ።
፲ ወይትዌከሉ ፡ ብከ ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ ያፈቅሩ ፡ ስመከ ።
እስመ ፡ ኢተኃድጎሙ ፡ ለእለ ፡ የኃሡከ ፡ እግዚኦ ።



ባትመለሱ ፡ ግን ፡ ሰይፉን ፡ ይመዛል ፡ ፲፪
ቀስቱንም ፡ ያነጣጥራል ።
የሞት ፡ መሣሪያንም ፡ አዘጋጀበት ፡ ፲፫
ፍላጻዎቹንም ፡ የሚቃጠሉ ፡ አደረገ ።
እነሆ ፡ አመፀኛ ፡ በዓመፃው ፡ ተጨነቀ ፡ ፲፬
ጉዳትን ፡ ፀነሰ ፡ ኃጢአትንም ፡ ወለደ ።
ጉድጓድን ፡ ማሰ ፡ ቆፈረም ፤ ፲፭
ባዘጋጀውም ፡ ጉድጓድ ፡ ይወድቃል ።
ጥፋቱ ፡ በራሱ ፡ ይመለሳል ፡ ፲፮
ዓመፃውም ፡ በአናቱ ፡ ላይ ፡ ትወርዳለች ።
እግዚአብሔርን ፡ እንደ፡ጽድቁ፡መጠን፡አመሰግነዋለሁ ፲፯
ለልዑል ፡ እግዚአብሔርም ፡ ስም ፡ እዘምራለሁ ።

መዝሙር ፡ ፰ ።

ትንቢት ፡ ስለክርስቶስ ።

አቤቱ ፡ ጌታችን ፡ ስምህ ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ እጅግ ፡ ተመሰገነ ፡ ፩
ምስጋናህ ፡ ከሰማዮች ፡ በላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብሎአልና ።
ጠላትን፡ ለማሳፈር፡ ቂመኛንና፡ ግፈኛንም፡ ለማጥፋት፡ ፪
ከሕፃናትና ፡ ከሚጠቡ ፡ ልጆች ፡ አፍ ፡ ምስጋናን ፡ አዘጋጀህ ።
የእጆችህን ፡ ሥራ ፡ ሰማዮችን ፡ እመለከታለሁ ፡ ፫
ጨረቃንና ፡ ከዋክብትንም ፡ አንተ ፡ ፈጥረሃቸዋልና ።
ታስበው ፡ ዘንድ ፡ ሰው ፡ ምንድር ፡ ነው ? ፬
ትጐበኘውስ ፡ ዘንድ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ምንድር ፡ ነው ።
ከመላእክት ፡ ይልቅ ፡ ጥቂት ፡ አሳነስኸው ፤ ፭
የክብርና ፡ የምስጋና ፡ ዘውድ ፡ አቀዳጀኸው ።
በእጆችህም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ሾምኸው ፡ ፮
ሁሉን ፡ ከእግሮቹ ፡ በታች ፡ አስገዛህለት ።
በጎችንም ፡ ላሞችንም ፡ ሁሉ፡ ፯
ደግሞም ፡ የምድረ ፡ በዳውን ፡ እንስሶች ።
የሰማይንም ፡ ወፎች ፡ የባሕርንም ፡ ዓሦች ፡ ፰
በባሕር ፡ ላይ ፡ የሚሄደውንም ፡ ሁሉ ።
አቤቱ፡ ጌታችን፡ሆይ፡ ስምህ፡ በምድር ፡ ሁሉ፡ ላይ፡ እጅግ ፡ ተመሰገነ። ፱

መዝሙር ፡ ፱ ።

ስለራሱ ፤ ስለግፈኞችና ፡ ስለተገፊዎች ።

አቤቱ ፡ በፍጹም ፡ ልቡናዬ ፡ አመሰግንሃለሁ ፡ ፩
ተአምራትህንም ፡ ሁሉ ፡ እነግራለሁ ።
በአንተ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፡ ሐሤትንም ፡ አደርጋለሁ ፡ ፪
ልዑል ፡ ሆይ ፡ ለስምህ ፡ እዘምራለሁ ።
ጠላቶቼ ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ በተመለሱ ፡ ጊዜ ፡ ፫
ይሰናከላሉ ፡ ከፊትህም ፡ ይጠፋሉ ።
ፍርዴን፡ ፈርደህልኛል፡ በቀሌንም፡ ተወጥተህልኛልና፡ ፬
ጽድቅን ፡ እየፈረድህ ፡ በዙፋንህ ፡ ላይ ፡ ተቀመጥህ ።
አሕዛብን ፡ ገሠጽህ ፡ ዝንጉዎችንም ፡ አጠፋህ ፡ ፭
ስማቸውንም ፡ ለዘላለም ፡ ደመሰስህ ።
ጠላቶች ፡ ለዘላለሙ ፡ በጦር ፡ ጠፉ ፡ ፮
ከተሞቻቸውንም ፡ አፈረስህ ፤
መታሰቢያቸውም ፡ በአንድነት ፡ ጠፋ ።
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ለዘላለም ፡ ይኖራል ፡ ፯
ለመፍረድም ፡ ዙፋኑን ፡ አዘጋጀ ።
እርሱም ፡ ዓለምን ፡ በጽድቅ ፡ ይፈርዳታል ፡ ፰
አሕዛብንም ፡ በትክክል ፡ ይዳኛቸዋል ።
እግዚአብሔር ፡ ለድሆች ፡ መጠጊያ ፡ ሆናቸው ፡ ፱
እርሱ ፡ በመከራቸው ፡ ጊዜ ፡ ረዳታቸው ፡ ነውና ።
ስምህን ፡ የሚያውቁ ፡ በአንተ ፡ ይታመናሉ ፡ ፲
አቤቱ ፡ የሚሹህን ፡ ሁሉ ፡ አትተዋቸውምና ።

፲፩ ዘምሩ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ዘየኀድር ፡ ውስተ ፡ ጽዮን ።
ወንግርዎሙ ፡ ለአሕዛብ ፡ ምግባሮ ።
፲፪ እስመ ፡ ተዘከረ ፡ ዘይትኃሠሥ ፡ ደሞሙ ።
ወኢረስዐ ፡ አውያቶሙ ፡ ለነዳያን ።
፲፫ ተሣሀለኒ ፡ እግዚኦ ፡ ወርኢ ፡ ዘከመ ፡ የኀሙኒ ፡ ጸላእትየ
፲፬ ዘያሌዕለኒ ፡ እምአናቅጸ ፡ ሞት ።
ከመ ፡ እንግር ፡ ኵሎ ፡ ስብሐቲሁ ።
በአናቅጺሃ ፡ ለወለተ ፡ ጽዮን ፡
ወንትፌሣሕ ፡ በአድኀኖትከ ።
፲፭ ጠግዑ ፡ አሕዛብ ፡ በጌጋዮሙ ፡ ዘገብሩ ።
ወበይእቲ፡መሥገርት፡እንተ፡ኀብኡ፡ተሠግረ፡እግሮሙ።
፲፮ የአምር ፡ እግዚአብሔር ፡ገቢረ ፡ ፍትሕ ።
ወበግብረ ፡ እደዊሁ ፡ ተሠግረ ፡ ኃጥእ ።
፲፯ ይግብኡ ፡ ኃጥአን ፡ ውስተ ፡ ሲኦል ።
ወኵሎሙ ፡ አሕዛብ ፡ እለ ፡ ይረስዕዎ ፡ ለእግዚአብሔር ።
፲፰ እስመ ፡ አኮ ፡ ለዝሉፉ ፡ ዘይትረሳዕ ፡ ነዳይ ።
ወኢየሀጕሉ ፡ ትእግሥቶሙ ፡ ነዳያን ፡ ለዓለም ።
፲፱ ተንሥእ ፡ እግዚኦ ፡ ወኢይጽናዕ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ።
ወይትኰነኑ ፡ አሕዛብ ፡ በቅድሜከ ።
፳ ሢም ፡ እግዚኦ ፡ መምህረ ፡ ሕግ ፡ ላዕሌሆሙ ።
ወያእምሩ፡አሕዛብ፡ከመ፡ዕጓለ፡እመሕያው፡እሙንቱ።
፳፩ ለምንት ፡ እግዚኦ ፡ ቆምከ ፡ እምርኁቅ ።
ወትትዔወር ፡ በጊዜ ፡ ምንዳቤየ ።
፳፪ በትዕቢቱ ፡ ለኃጥእ ፡ ይውዒ ፡ ነዳይ ።
ወይሠገሩ ፡ በውዴቶሙ ፡ እንተ ፡ ሐለዩ ።
፳፫ እስመ ፡ ይትዌደስ ፡ ኃጥእ ፡ በፍትወተ ፡ ነፍሱ ።
ወዐማፂኒ ፡ ይትባረክ ።
፳፬ ወሐኮ ፡ ኃጥእ ፡ ለእግዚአብሔር ።
ወኢይትኃሠሦ ፡ በከመ ፡ ብዝኃ ፡ መዓቱ ።
ወአልቦ ፡ እግዚአብሔር ፡በቅድሜሁ ።
፳፭ ወርኵስ ፡ ኵሉ ፡ ፍናዊሁ ።
ወንሡት ፡ ኵነኔከ ፡ በቅድሜሁ ።
ወይቀንዮሙ ፡ ለኵሎሙ ፡ ጸላእቱ ።
፳፮ ወይብል ፡ በልቡ ፡ ኢይትሀወክ ፡ ለትውልደ ፡
ትውልድ ፡ ወኢይረክበኒ ፡ እኩይ ።
፳፯ ምሉዕ ፡ አፉሁ ፡ መርገመ ፡ ወጽልሑተ ።
ታሕተ ፡ ልሳኑ ፡ ፃማ ፡ ወሕማም ።
፳፰ ይጸንሕ ፡ ወይንዑ ፡ ምስለ ፡ ብዑላን ።
ከመ ፡ ይቅትሎ ፡ ለንጹሕ ፡ በጽሚት ።
ወአዕይንቲሆሙኒ ፡ ኀበ ፡ ነዳይ ፡ ያስተሐይጻ ።
፳፱ ይጸንሕ ፡ ወይትኀባእ ፡ ከመ ፡ አንበሳ ፡ ውስተ ፡ ግብ
ይጸንሕ ፡ ከመ ፡ ይምሥጦ ፡ ለነዳይ ፡
ይመስጦ ፡ ለነዳይ ፡ ወይስሕቦ ።
ወያኀስሮ ፡ በመሥገርቱ ።
፴ ይትቀጻዕ ፡ ወይወድቅ ፡ ሶበ ፡ ቀነዮ ፡ ለነዳይ ።
፴፩ ወይብል ፡ በልቡ ፡ ይረስዐኒ ፡ እግዚአብሔር ።
ወሜጠ ፡ ገጾ ፡ ከመ ፡ ኢይርአይ ፡ ለግሙራ ።
፴፪ ተንሥእ ፡ እግዚኦ ፡ አምላኪየ ፡ ወትትለዐል ፡ እዴከ
ወኢትርስዖሙ ፡ ለነዳያን ።
፴፫ በእንተ ፡ ምንት ፡ አምዕዖ ፡ ኃጥእ ለእግዚአብሔር ።
እስመ ፡ ይብል ፡ በልቡ ፡ ኢይትኃሠሠኒ ።
፴፬ ትሬኢ ፡ ከመ ፡ ለሊከ ፡ ትኔጽር ፡ ፃማ ፡ ወመዓተ ።
ወከመ ፡ ትሜጥዎ ፡ ውስተ ፡ እዴከ ።
ላዕሌከኑ ፡ እንከ ፡ ተገድፈ ፡ ነዳይ ።
ወአንተኑ ፡ ረዳኢሁ ፡ ለዕጓለ ፡ ማውታ ።
፴፭ ቀጥቅጥ ፡ መዝራዕቶ ፡ ለኃጥእ ፡ ወለእኩይ ።
ወትትኀሠሥ ፡ ኀጢአቱ፡በእንቲአሁ፡ ወኢትትረከብ
፴፮ ይነግሥ ፡እግዚአብሔር ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ።
ወይትኀጐሉ ፡ አሕዛብ ፡ እምድር ።



በጽዮን ፡ ለሚኖር ፡ ለእግዚአብሔር ፡ዘምሩ ፡ ፲፩
በአሕዛብም ፡ መካከል ፡ ሥራውን ፡ ንገሩ ።
የድሆችን ፡ ጩኸት ፡ ሳይዘነጋ ፤ ፲፪
ደማቸውን ፡ ይመራመር፡ዘንድ፡ እርሱ ፡ አስቦአልና ።
አቤቱ፡አዘንልኝ፡ጠላቶቼም፡የሚያመጡብኝን፡መከራ፡ሁሉ፡ተመልከት፡ ፲፫
ከሞት ፡ አፋፍ ፡ የምትመልሰኝ ፡ የአንተን ፡ ፲፬
ምስጋናህን ፡ ሁሉ ፡ እናገር ፡ ዘንድ ፤
በጽዮን ፡ ልጅ ፡ በአዳባባይዋ ፡
በማዳንህ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ።
አሕዛብ ፡ በቈፈሩት ፡ ጕድጓድ ፡ ወደቁ ፡ ፲፭
በዚያችም፡በሸሸጓት፡ወጥመድ፡እግራቸው፡ተጠመደች።
እግዚአብሔር ፡ ዕውነትን፡በመፍረድ፡የታወቀ፡ነው ፤ ፲፮
ኃጢአተኛ እራሱ ፡ ባጠመደው ፡ ወጥመድ ፡ ተጠመደ ።
ኃጢአተኞች ፡ ወደ ፡ ሲኦል ፡ ይወርዳሉ ፡ ፲፯
እግዚአብሔርንየሚረሱ፡አሕዛብም፡ሁሉ፡ይከተሏቸዋል።
ድሀ ፡ ግን ፡ ለዘላለም ፡ አይረሳምና ፡ ፲፰
የችግረኞችም ፡ ተስፋቸው ፡ ለዘላለም ፡ አይጠፋም።
አቤቱ ፡ ተነሥ ፤ ጠላትም ፡ አይበርታ ፤ ፲፱
አሕዛብም ፡ በፊትህ ፡ ይፈረድባቸው ።
አቤቱ ፡ ፍርሃትን ፡ በላያቸው ፡ ጫንባቸው ፤ ፳
አሕዛብም ፡ ሰብአዊ፡ ፍጡሮች፡ እንደ፡ ሆኑ፡ ይወቁ ።
አቤቱ ፡ ለምን ፡ ርቀህ ፡ ቆምህ ? ፳፩
በመከራስ ፡ ጊዜ ፡ ለምን ፡ ትሰወራለህ ?
በኃጢአተኛ ፡ ትዕቢት ፡ ድሀ ፡ ይበሳጫልና ፡ ፳፪
ባሰቡት ፡ ተንኰላቸው ፡ ተጠመዱ ።
ኃጢአተኛ ፡ በነፍሱ ፡ ፈቃድ ፡ ይወደሳልና ፡ ፳፫
ዓመፀኛም ፡ ሊመሰገን ፡ ይወዳልና ።
ኃጢአተኛ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አስቈየመው ፡ ፳፬
እንደ ፡ ቍጣው ፡ ብዛት፡ግን ፡ አይመራመረውም ፡
በእርሱ ፡ ዘንድ ፡እግዚአብሔር እንደሌለ ፡ ያስባል ።
መንገዱ ፡ ሁሉ ፡ የረከሰ ፡ ነው ፡ ፳፭
ጠላቶችንም ፡ ሁሉ ፡ ስለሚገዛቸው ፡
ፍርድህ ፡ በፊቱ ፡ ቀላል ፡ ይመስለዋል ።
በልቡም፡ ለልጅ፡ ልጅ፡ አልታወክም፡ ክፉም፡ አያገኘኝም፡ ይላል። ፳፮
አፉ፡መርገምን፡ ሽንገላንና፡ ተንኰልን፡ የተመላ፡ ነው ፤ ፳፯
በአንደበቱ ፡ ጉዳትና ፡ መከራን ፡ ይጠራል ።
ንጹሓንን ፡ በስውር ፡ ይገድል ፡ ዘንድ ፤ ፳፰
በመንደሮች ፡ መካከል ፡ መሸመቂያ ፡ ያዘጋጃል ፡
ዓይኖቹም ፡ ወደ ፡ ድኃ ፡ ይመለከታሉ ።
እንደ ፡ አንበሳ ፡ በጫካ ፡ ውስጥ ፡ በስውር፡ተሸምቆ ፡ ፳፱
ድሀውን ፡ ለመንጠቅ ፡ ያደባል ፤
ድሀውን ፡ ይነጥቀዋል ፡ በአሽክላውም ፡ ይጐትተዋል ።
ድሀው ፡ ይጐነበሳል ፡ ይጐብጥማል ፤ ፴
በኃያላኑም ፡ እጅ ፡ ይወድቃል ።
በልቡም ፡ እግዚአብሔር ፡ረስቶኛል ፡ እስከ ፡ ማለትም ፡ ይደርሳል ፤ ፴፩
ፊቱንም ፡ እንዳያይ ፡ ፊቱን ፡ አዞረ ፡ ይላል ።
አቤቱ፡አምላክ፡ሆይ፡ተነሥ፡ክንድህም፡ከፍ፡ከፍ ትበል፤ ፴፪
ድሆችንም ፡ አትርሳ ።
ኃጢአተኛ፡ ስለምን ፡ እግዚአብሔርን ፡ አስቆጣው ? ፴፫
በልቡ ፡ አይመራመረኝም ፡ ይላልና ።
በእጅህ ፡ ብድራቱን ፡ ለመክፈል ፡ እነሆ ፡ አየኸው ፡ ፴፬
አንተ ፡ ክፋትንና ፡ ቍጣን ፡ ትመለከታለህና ፤
ድሀ ፡ እምነቱን ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ ይጥላል ፤
ለድሀ ፡ አደግም ፡ ረዳቱ ፡ አንተ ፡ ነህ ።
አንዳችም ፡ ነገር እስከማይቀር ፡ ድረስ ፡ ፴፭
የኃጢአተኛንና ፡ የክፉን ፡ ክንድ ፡ ሰበር ፤
የኃጢአቱንም ፡ ብድራት ፡ ክፈል ።
እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ ይነግሣል ፤ ፴፮
አሕዛብም ፡ ከምድር ፡ ይጠፋሉ ።

፴፯ ፍትወቶሙ ፡ ለነዳያን ፡ ሰምዐ ፡ እግዚአብሔር ፡
ወሕሊና ፡ ልቦሙ ፡ አጽምዐት ፡ እዝኑ ።
፴፰ ፍትሑ ፡ ለነዳይ ፡ ወለዕጓለ ፡ ማውታ ።
ከመ ፡ ኢይድግሙ ፡ እንከ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ፡
አዕብዮ ፡ አፉሆሙ ፡ በዲበ ፡ ምድር ።

## መዝሙር ፡ ፲ ።

በእንተ ፡ ፍጻሜ ፡ ወበእንተ ፡ ሲሞን ፡ ወኢያሶን ።

፩ በእግዚአብሔር ፡ ተወከልኩ፡እፎ ፡ ትብልዋ ፡ለነፍስየ
አዕይል ፡ ውስተ ፡ አድባር ፡ ከመ ፡ ዖፍ ።
፪ እስመ ፡ ናሁ ፡ ኃጥአን ፡ ወሰቁ ፡ ቀስቶሙ ።
ወአስተዳለዉ ፡ አሕጻቲሆሙ፡ውስተ ፡ ምጒንጳቲሆሙ
ከመ ፡ ይንድፍዎሙ ፡ ለርቱዓነ ፡ ልብ ፡ በጽሚት ።
፫ እስመ ፡ ናሁ ፡ ዘአንተ ፡ ሠራዕከ ፡ እሙንቱ ፡ ነሠቱ ።
ወጻድቅሰ ፡ ምንተ ፡ ገብረ ።
፬ እግዚአብሔር፡ ውስተ ፡ ጽርሐ ፡ መቅደሱ ።
እግዚአብሔር ፡ ውስተ ፡ ሰማይ ፡ መንበሩ ።
ወአዕይንቲሁ ፡ ኀበ ፡ ነዳይ ፡ ይኔጽራ ።
ወቀራንብቲሁ ፡ የሐቱ ፡ ለዕጓለ ፡ እመሕያው ።
፭ እግዚአብሔር ፡ የሐትቶ ፡ ለጻድቅ ፡ ወለኃጥእ ።
ዘሰ ፡ አፍቀራ ፡ ለዐመፃ ፡ ጸልአ ፡ ነፍሶ ።
፮ ይዘንም ፡ መሣግረ ፡ ላዕለ ፡ ኃጥአን ።
እሳት ፡ ወተይ፡መንፈሰ፡ዐውሎ ፡ መክፈልተ፡ጽዋዖሙ
፯ እስመ ፡ ጻድቅ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወጽድቀ ፡ አፍቀረ ።
ወርትዕሰ ፡ ትሬእዮ ፡ ገጾ ።

## መዝሙር ፡ ፲፩ ።

ትንቢት ፡ በእንተ ፡ ሳምኒት ፡ ዘመን ።

፩ አድኅነኒ ፡እግዚኦ ፡ እስመ ፡ ኀልቀ ፡ ኄር ።
ወውኅደ ፡ ሃይማኖት ፡ እምዕጓለ ፡ እመሕያው ።
፪ ከንቶ ፡ ይትናገሩ ፡ አሐዱ ፡ ምስለ ፡ ካልኡ ።
በከናፍረ ፡ ጕሕሉት ፡ ልበ ፡ ወበልብ ፡ ይትናገሩ ።
፫ ይሤርዎን ፡ እግዚአብሔር ፡ ለከናፍረ ፡ ጕሕሉት ።
ወለልሳን ፡ እንተ ፡ ተዐቢ ፡ ነቢበ ።
፬ እለ ፡ ይብሉ ፡ ናዐቢ ፡ ልሳናቲነ ።
ወከናፍሪነኒ ፡ ኀቤነ ፡ እሙንቱ ።
፭ መኑ ፡ ውእቱ ፡ እግዚእነ ፡ በእንተ ፡ ሕማሞሙ ፡ ለነዳያን
ወበእንተ ፡ ገዓሮሙ ፡ ለሙቁሓን ።
ይእዜ ፡ እትነሣእ ፡ ይቤ ፡ እግዚአብሔር ።
እሬሲ ፡ መድኃኒተ ፡ ወአግህድ ፡ ቦቱ ።
ቃለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ንጹሕ ።
፮ ከመ ፡ ብሩር ፡ ጽሩይ ፡ ንጡፍ ፡ ወፍቱን ፡ እምድር ።
ዘአጽረይዎ ፡ ምስብዒተ ።
፯ አንተ ፡ እግዚኦ ፡ ዕቀበነ ፡ ወተማኅፀነነ ።
እምዛቲ ፡ ትውልድ ፡ ዘለዓለም ።
ዐውደ ፡ የሐውሩ ፡ ረሲዓን ።
፰ ወበከመ ፡ ዕበየ ፡ ልዕልናከ ፡ ሠራዕከሙ ፡ ለደቂቀ ፡
ዕጓለ ፡ እመሕያው ።

## መዝሙር ፡ ፲፪ ።

በእንተ ፡ ትሩፋን ፡ መዘርእሱ ።

፩ እስከ ፡ ማእዜኑ ፡ እግዚኦ ፡ ትረስዐኒ ፡ ለግሙራ ።
እስከ ፡ ማእዜኑ ፡ ትመይጥ ፡ ገጸከ ፡ እምኔየ ።



እግዚአብሔር ፡ የድሆችን ፡ ቃል ፡ ሰማ ፡ ፴፯
ጆሮውም ፡ የልባቸውን ፡ አሳብ ፡ አደመጠች ፡
ሰዎች፡ በምድር፡ ላይ፡ አፋቸውን ፡ ከፍ፡ ከፍ ፡ማድረግ፡እንዳይደግሙ ፡ ፴፰
ፍርዱ፡ለድሀ፡አደግና፡ለችግረኛ፡ይደረግ፡ዘንድ፡ነውና ።

## መዝሙር ፡ ፲ ።

ስለራሱ ፡ ስለሲሞንና ፡ ኢያሶን ።

በእግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ ታመንሁ ፡ ፩
ነፍሴን፡ እንደ ፡ ወፍ፡ወደ ፡ ተራሮች፡ተቅበዝበዢ፡እንዴት፡ ትሏታላችሁ
ልበ ፡ ቅኖችን ፡ በስውር ፡ ይነድፉ ፡ ዘንድ ፡ ፪
ኃጢአተኞች ፡ እነሆ ፡ ቀስታቸውን ፡ አነጣጥረዋልና ፡
ፍላጻቸውንም ፡ በአውታር ፡ አዘጋጅተዋልና ።
ጻድቅ ፡ ግን ፡ ምን ፡ አደረገ ? አንተ ፡ የሠራኸውን ፡ ፫
እነሆ ፡ እነርሱ ፡ ሊያጠፉ ፡ ይሻሉና ፤
እግዚአብሔር ፡ በተቀደሰው ፡ መቅደሱ ፡ ነው ፤ ፬
እግዚአብሔር ፡ ዙፋኑ ፡ በሰማይ ፡ ነው ፤
ዓይኖቹም ፡ ወደ ፡ ድሀ ፡ ይመለከታሉ ።
ቅንድቦቹም ፡ የሰው ፡ ልጆችን ፡ ይመረምራሉ ።
እግዚአብሔር ፡ ጻድቅንና ፡ ኃጥአንን ፡ ይመረምራል ፤ ፭
ዓመፃን ፡ የወደዳት ፡ ነፍሱን ፡ ጠልቶአል ።
የወጥመድ ፡ ዝናም ፡ በኃጥአን ፡ ላይ ፡ ያዘንማል ፡ ፮
እሳትና ፡ ዲን ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስም ፡ የጽዋቸው ፡ ፈንታ ፡ ነው ።
እግዚአብሔር ፡ ጻድቅ ፡ ነውና ፡ ጽድቅን ፡ ይወዳል ፤ ፯
ቅንነትም ፡ ፊቱን ፡ ታየዋለች ።

## መዝሙር ፡ ፲፩ ።

ስለስምንተኛው ፡ ሺህ ፡ ዘመን ።

አቤቱ ፡ አድነኝ ፤ ደጋግ ፡ ሰዎች ፡ አልቀዋልና ፡ ፩
ከሰው ፡ ልጆችም ፡ መተማመን ፡ ጠፍቷልና ።
እርስ ፡ በራሳቸው ፡ ከንቱ ፡ ነገርን ፡ ይናገራሉ ፡ ፪
በመሸንጋገልና ፡ በመዳለል ፡ ከንፈር ፤
ሁለት ፡ ልብ ፡ ሆነው ፡ ይናገራሉ ።
ዳሩ ፡ ግን ፡ የሸንገላን ፡
ከንፈሮች ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያጠፋቸዋል፤ ፫
ከንፈራችን ፡ የእኛ ፡ ነው ፡ ጌታችን ፡ ማን ፡ ነው ?
ከፍተኛውን ፡ ነገር ፡ መናገር ፡ የምትችለውንም ፡ ፬
አንደበት ፡ እናበረታለን ፡ የሚሉትንም ፤
ይደመስሳቸዋል ።
ስለ ፡ ድሆች ፡ መከራ ፡
ስለ ፡ ችግረኞችም ፡ ጩኸት ፡ መድኃኒትን ፡ ለማድረግ ፡
ኃይሉንም ፡ ለመግለጽ ፡ እግዚአብሔር ፡ አሁን ፡ ፭
እነሣለሁ ፡ ይላል ።
በምድር ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ተፈተነ ፡ ሰባት ፡ ጊዜም ፮
ነጥሮ ፡ እንደ ፡ ተጣራ ፡ ብር ፤
የእግዚአብሔር ፡ ቃላት ፡ የነጹ ፡ ናቸው ።
አቤቱ ፡ አንተ ፡ ጠብቀን ፡ ፯
ከዚህችም ፡ ትውልድ ፡ ለዘላለም ፡ ታደገን ።
በሰው ፡ ልጆች ፡ ዘንድ ፡ ምናምንቴ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ ፰
ክፉዎች ፡ በዙሪያው ፡ ሁሉ ፡ ይመላለሳሉና ።

## መዝሙር ፡ ፲፪ ።

ስለራሱና ፡ ስለትሩፋን ።

አቤቱ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ፈጽመህ ፡ ትረሳኛለህ ? ፩
እስከ ፡ መቼስ ፡ ፊትህን ፡ ከእኔ ፡ ትሰውራለህ ፡

፪ እስከ ፡ ማእዜኑ ፡ አነብር ፡ ኀዘነ ፡ ውስተ ፡ ነፍስየ ።
ወትጼዕረኒ ፡ ልብየ ፡ ኵሎ ፡ አሚረ ።
እስከ ፡ ማእዜኑ ፡ ይትዔበዩ ፡ ጸላእትየ ፡ ላዕሌየ ።
፫ ነጽረኒ ፡ ወስምዐኒ ፡ እግዚኦ ፡ አምላኪየ ።
አብርሆን ፡ ለአዕይንትየ ፡ ከመ ፡ ኢይኑማ ፡ ለመዊት ።
ወከመ ፡ ኢይበሉኒ ፡ ጸላእትየ ፡ ሞዕናሁ ።
፬ ወእለሰ ፡ ይሣቅዩኒ ፡ ይትፌሥሑ ፡ ለእመ ፡ ተሀወኩ ።
፭ ወአንሰ ፡ በምሕረትከ ፡ ተወከልኩ ።
ይትፌሥሐኒ ፡ ልብየ ፡ በአድኅኖትከ ።
፮ እሴብሖ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ዘረድአኒ ።
ወእዜምር ፡ ለስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ልዑል ።

መዝሙር ፡ ፲፫ ።

በእንተ ፡ ሕዝቅያስ ፡ አመ ፡ አገቶ ፡ ሰናክሬም ።

፩ ይብል ፡ አብድ ፡ በልቡ ፡ አልቦ ፡ እግዚአብሔር ።
ኀበሱ ፡ ወረኵሱ ፡ በምግባሪሆሙ ።
አልቦ ፡ ዘይገብራ ፡ ለሠናይት ፡ አልቦ ፡ ወኢአሐዱ ።
፪ እግዚአብሔር ሐወጸ፡እምሰማይ፡ላዕለ፡ዕጓለ፡እመሕያው
ከመ፡ይርአይ፡እመቦ፡ጠቢብ፡ዘየኀሥሥ፡
፫ ኵሉ ፡ ዐረየ ፡ ወኅቡረ ፡ ዐለወ ።
አልቦ ፡ ዘይገብራ ፡ ለሠናይት ፡ አልቦ ፡ ወኢአሐዱ ።
፬ ከመ ፡ መቃብር ፡ ክሡት ፡ ጐራዒቶሙ ።
ወጸልሐዉ ፡ በልሳናቲሆሙ ።
፭ ሕምዘ ፡ አርዌ ፡ ምድር ፡ ታሕተ ፡ ከናፍሪሆሙ ።
መሪር ፡ አፉሆሙ ፡ ወምሉዕ ፡ መርገመ ።
፮ በሊዓ ፡ እገሪሆሙ ፡ ለክዒወ ፡ ደም ።
ኀሣር ፡ ወቅጥቃጤ ፡ ውስተ ፡ ፍኖቶሙ ።
ኢየአምርዋ ፡ ለፍኖተ ፡ ሰላም ።
ወአልቦ፡ፍርሀተ እግዚአብሔር ቅድመ፡አዕይንቲሆሙ
ወኢየአምሩ ፡ ኵሎሙ ፡ ገበርተ ፡ ዐመፃ ።
፯ እለ ፡ ይውኅጥዎሙ ፡ ለሕዝብየ ፡ ከመ ፡ በሊዐ ፡ እክል ።
ወለእግዚአብሔርሰ ፡ ኢጸውዕዎ ።
፰ ወበህየ ፡ ፈርሁ ፡ ወገረሞሙ ፡ ዘኢኮነ ፡ ግሩመ ።
እስመ እግዚአብሔር ፡ ውስተ ፡ ትውልደ ፡ ጻድቃን ።
፱ ወአስተኀፈርክሙ ፡ ምክረ ፡ ነዳይ ።
እስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተስፋሆሙ ፡ ውእቱ ።
፲ መኑ ፡ ይሁብ ፡ መድኀኒተ ፡ እምጽዮን ፡ ለእስራኤል ።
አመ ፡ ሜጠ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፄዋ ፡ ሕዝቡ ።
ይትፌሣሕ ፡ ያዕቆብ ፡ ወይትሐሠይ ፡ እስራኤል ።

መዝሙር ፡ ፲፬ ።

በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ እግዚኦ ፡ መኑ ፡ የኀድር ፡ ውስተ ፡ ጽላሎትከ ።
ወመኑ ፡ ያጸልል ፡ ውስተ ፡ ደብረ ፡ መቅደስከ ።
፪ ዘየሐውር ፡ በንጹሕ ፡ ወይገብር ፡ ጽድቀ ።
ወዘይነብብ ፡ ጽድቀ ፡ በልቡ ።
፫ ወዘኢጓሕለወ ፡ በልሳኑ ።
ወዘኢገብረ ፡ እኩየ ፡ ዲበ ፡ ቢጹ ።
ወዘኢያጽዐለ ፡ አዝማዲሁ ።
፬ ወዘምኑን ፡ በቅድሜሁ ፡ እኩይ ።
ዘያከብሮሙ ፡ ለፈራህያነ ፡ እግዚአብሔር ።
ዘይምሕል ፡ ለቢጹ ፡ ወኢይሔሱ ።
፭ ወዘኢለቅሐ ፡ ወርቆ ፡ በርደ ።
ወዘኢነሥአ ፡ ሕልያነ ፡ በላዕለ ፡ ንጹሕ ።
ዘይገብር ፡ ከመዝ ፡ ኢይትሀወክ ፡ ለዓለም ።



እስከ ፡ መቼ ፡ በነፍሴ ፡ እብከነከናለሁ ? ፪
ትካዜስ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ሁል፡ ጊዜ ፡ ይሆናል ?
እስከ ፡ መቼ ፡ ጠላቴ ፡ በኔ፡ ላይ ፡ ይገናናል ።
ጠላቴ ፡ አሸነፍሁት ፡ እንዳይል ፡ ፫
አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ እየኝ ፡ ስማኝም ።
የሚያስጨንቁኝም፡ እኔ፡ ብናወጥ፡ደስ፡እንዳይላቸው ፡ ፬
እስከሞትም ፡ እንዳልተኛ ፡ ዓይኖቼን፡ አብራ ።
እኔ ፡ ግን ፡ በቸርነትህ ፡ ታመንሁ ፡ ፭
ልቤም ፡ በመድኃኒትህ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ።
የረዳኝን ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰግናለሁ ፡ ፮
ለልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡ ስምም ፡ እዘምራለሁ ።

መዝሙር ፡ ፲፫ ።

ስለሕዝቅያስና ፡ ስለሰናክሬም ።

ሰነፍ ፡ በልቡ ፡ እግዚአብሔር ፡ የለም ፡ ይላል ፤ ፩
በሥራቸው ፡ ረከሱ ፡ ጐሰቈሉም ፤
በጎ ፡ ነገርን ፡ የሚሠራ ፡ የለምና ።
የሚያስተውል፡እግዚአብሔርንም ፡ የሚፈልግ፡ እንዳለ፡ ያይ፡ ዘንድ ፡ ፪
እግዚአብሔር፡ ከሰማይ ፡ የሰው ፡ ልጆችን፡ ተመለከተ ።
ሁሉ ፡ ዐመፁ ፡ በአንድነትም ፡ ረከሱ ፤ ፫
በጎ ፡ ነገርን ፡ የሚሠራ ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፡ የለም ።
ጕረሯቸው ፡ የተከፈተ ፡ መቃብር ፡ ነው ፡ ፬
በአንደበታቸው ፡ ይሸነግላሉ ፡
ከከንፈራቸው ፡ በታች ፡ ግን ፡ የእባብ ፡ መርዝ ፡ አለ ፡ ፭
አፋቸው ፡ መርገምንና ፡ መራራን ፡ የተመላ ፡ ነው ።
ደምን ፡ ለማፍሰስ ፡ እግራቸው ፡ ፈጣን ፡ ነው ፤ ፮
ጥፋትና ፡ ጕስቍልና ፡ በመንገዳቸው ፡ ላይ ፡ አለ ፤
የሰላምን ፡ መንገድ ፡ አያውቁምና ፤
በነሱ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ የለም ።

ሕዝቤን ፡ እንደ ፡ እንጀራ ፡ የሚበሉ ፤ ፯
ኃጢአትንም ፡ የሚሠሩ ፡ ሁሉ፡ በውኑ ፡ አያውቁምን ?
እግዚአብሔርንም ፡ አይጠሩትም ።
ነገር ፡ ግን፡በዚያን፡ጊዜ፡ታላቅ፡ፍርሃት፡ይወድቅባቸዋል፡ ፰
እግዚአብሔር፡ በጻድቃን ፡ ትውልድ ፡ ዘንድ ፡ ነውና ።
የድሆችን ፡ ምክር ፡ ለማፍረስ ፡ ትጥራላችሁ ፡ ፱
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ተስፋቸው ፡ ነው ።
ከጽዮን ፡ መድኃኒትን ፡ ለእስራኤል ፡ ማን ፡ ይልክል ? ፲
እግዚአብሔር ፡ የሕዝቡን ፡ ምርኮ ፡ በመለሰ ፡ ጊዜ ፤
ያዕቆብ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፡
እስራኤልም ፡ ሐሤትን ፡ ያደርጋል ።

መዝሙር ፡ ፲፬ ።

ስለ ትሩፋን ።

አቤቱ ፡ በድንኳንህ ፡ ውስጥ፡ ማን ፡ ያድራል ? ፩
በተቀደሰውም ፡ ተራራህ ፡ ማን ፡ ይኖራል ?
ነገር፡ ግን፡በቅንነት ፡ የሚሄድ፡ ጽድቅንም፡ የሚያደርግ፤ ፪
በልቡ ፡ በጎ ፡ ሃሳብ፡ ያለው ።
በአንደበቱ ፡ ሸንገላን ፡ የማይናገር ፤ ፫
በባልንጀራው ፡ ላይ ፡ ክፋትን ፡ የማያደርግ ፡
ዘመዶቹንም ፡ የማይሰድብ ።
ኃጢአተኛ ፡ በፊቱ ፡ የተናቀ ፤ ፬
እግዚአብሔርንም ፡ የሚፈሩትን ፡ የሚያከብር ፤
ለባልንጀራው ፡ የገባውን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ የማይከዳ ።
ገንዘቡን ፡ በአራጣ ፡ የማያበድር ፡ ፭
በንጹሑ ፡ ላይ ፡ መማለጃን ፡ የማይቀበል ፤
ሌላም ፡ እንዲህ ፡ የሚያደርግ ፡ እሱ ፡
ለዘላለም ፡ አይታወክም ።

መዝሙር ፡ ፲፭ ።

በእንተ ፡ ርእሱ ።

፩ ዕቀበኒ ፡ እግዚኦ ፡ እስመ ፡ ኪያከ ፡ ተወከልኩ ።
፪ እቤሎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እግዚእየ ፡ አንተ ።
እስመ ፡ ኢትፈቅዳ ፡ ለሠናይትየ ።
፫ ለቅዱሳን ፡ እለ ፡ ውስተ ፡ ምድር ።
ተሰብሐ ፡ ኵሉ ፡ ሥምረትከ ፡ በላዕሌሆሙ ።
፬ በዝኀ ፡ ደዌሆሙ ፡ ወእምዝ ፡ አስተፋጠኑ ።
ወኢይትጋበር ፡ ውስተ ፡ ማኅበሮሙ ፡ ዘደም ።
ወኢይዜክር ፡ አስማቲሆሙ ፡ በአፉየ ።
፭ እግዚአብሔር ፡ መክፈልተ ፡ ርስትየ ፡ ወጽዋዕየ ።
አንተ ፡ ውእቱ ፡ ዘታገብእ ፡ ሊተ ፡ ርስትየ ።
፮ አሕባለ ፡ ወረዉ ፡ ሊተ ፡ የአኀዙኒ ።
ወርስትየሰ ፡ እኁዝ ፡ ወኢቱ ፡ ሊተ ።
፯ እባርኮ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ዘአለበወኒ ።
ወዓዲ ፡ ሌሊተኒ ፡ ገሠጹኒ ፡ ኵልያትየ ።
፰ ዘልፈ ፡ አሬእዮ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቅድሜየ ፡ ውእቱ ፡ በኵሉ ፡ጊዜ ።
እስመ ፡ በየማንየ ፡ ውእቱ ፡ ከመ ፡ ኢይትሀወክ ።
፱ በእንተዝ ፡ ተፈሥሐ ፡ ልብየ ፡ ወተሐሥየ ፡ ልሳንየ ።
ወዓዲ ፡ በተስፋሁ ፡ ኀደረ ፡ ሥጋየ ።
፲ እስመ ፡ ኢተኀድጋ ፡ ውስተ ፡ ሲኦል ፡ ለነፍስየ ።
ወኢትሁብ ፡ ለጻድቅከ ፡ ይርአይ ፡ ሙስና ።
፲፩ ወአርአይከኒ ፡ ፍኖተ ፡ ሕይወት ።
ወአጽገብከኒ ፡ ሐሤተ ፡ ምስለ ፡ ገጽከ ።
ወትፍሥሕት ፡ ውስተ ፡ የማንከ ፡ ለዝሉፉ ።

መዝሙር ፡ ፲፮ ።

በእንተ ፡ ርእሱ ።

፩ እግዚኦ ፡ ስምዐኒ ፡ ጽድቅየ ።
ወአጽምዐኒ ፡ ስእለትየ ።
ወአጽምዐኒ ፡ ጸሎትየ ፡ ዘኢኮነ ፡ በከናፍረ ፡ ጕሕሉት ።
፪ እምቅድመ ፡ ገጽከ ፡ ይወፅእ ፡ ፍትሕየ ።
አዕይንትየኒ ፡ ርእያ ፡ ጽድቀከ ።
፫ ሐወጽከኒ ፡ ሌሊተ ፡ ወፈተንከ ፡ ለልብየ ።
አመከርከኒ ፡ ወኢተረክበ ፡ ዐመፃ ፡ በላዕሌየ ።
፬ ከመ ፡ ኢይንብብ ፡ አፉየ ፡ ግብረ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ።
በእንተ ፡ ቃለ ፡ ከናፍሪከ ።
አነ ፡ ዐቀብኩ ፡ ፍኖወ ፡ ዕፁባተ ።
፭ አጽንዖን ፡ ለመከየድየ ፡ ውስተ ፡ ፍኖትከ ።
ከመ ፡ ኢይድኀፅ ፡ ሰኰናየ ።
፮ አንሰ ፡ ጸራኅኩ ፡ እስመ ፡ ሰምዐኒ ፡ እግዚአብሔር ።
አጽምዕ ፡ እዝነከ ፡ ኀቤየ ፡ ወስምዐኒ ፡ ቃልየ ።
ሰብሖ ፡ ለምሕረትከ ።
፯ ዘያድኅኖሙ ፡ ለእለ ፡ ይትዌከሉከ ።
እምእለ ፡ ይትቃወምዋ ፡ ለየማንከ ።
፰ ዕቀበኒ ፡ ከመ ፡ ብንተ ፡ ዐይን ።
ወበጽላሎተ ፡ ክነፊከ ፡ ክድነኒ ።
፱ እምገጸ ፡ ኃጥኣን ፡ እለ ፡ ያኀስሩኒ ።
ጸላእትየሰ ፡ አስተሐየጽዋ ፡ ለነፍስየ ።
፲ ወቈጸሩ ፡ አማዑቶሙ ።
ወነበበ ፡ ትዕቢተ ፡ አፉሆሙ ።
፲፩ ሰደዱኒ ፡ ይእዜ ፡ ዐገቱኒ ።
ወአትሐቱ ፡ አዕይንቲሆሙ ፡ ውስተ ፡ ምድር ።
፲፪ ወተመጠዉኒ ፡ ከመ ፡ አንበሳ ፡ ዘጽኑሕ ፡ ለመሢጥ ።
ወከመ ፡ ዕጓለ ፡ አንበሳ ፡ ዘይነብር ፡ ተኀቢኦ ።



መዝሙር ፡ ፲፭ ።

ስ ለ ራ ሱ ።

አቤቱ ፡ በአንተ ፡ ታምኛለሁና ፡ ጠብቀኝ ። ፩
እግዚአብሔርን ፡ አንተ ፡ ጌታዬ ፡ ነህ ፡ አልሁ ፤ ፪
ከአንተ ፡ በቀር ፡ በጎነት ፡ የለኝም ።
ፈቃድህ ፡ በምድር ፡ ባሉት ፡ ቅዱሳንና ፡ ፫
ክቡራን ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ነው ።
ወደ ፡ ሌላ ፡ ለሚፋጠኑት ፡ መከራቸው ፡ ይበዛል ፤ ፬
በቍርባናቸው ፡ ደም ፡ እኔ ፡ አልተባበራቸውም ፤
ስማቸውንም ፡ በከንፈሬ ፡ አልጠራም ።
እግዚአብሔር ፡ የርስቴ ፡ እድል ፡ ፈንታና ፡ ጽዋዬ ፡ ነው ፭
ድርሻዬንም ፡ የምትሰጠኝ ፡ አንተ ፡ ነህ ።
ገመድ ፡ ባማረ ፡ ስፍራ ፡ ወደቀችልኝ ፤ ፮
ርስቴም ፡ ተደለደለችልኝ ።
የመከረኝን ፡ እግዚአብሔርን ፡ እባርካለሁ ፤ ፯
ደግሞም ፡ በሌሊት ፡ ኵላሊቶቼ ፡ ይገሥጹኛል ።
ሁል ጊዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡ በፊቴ ፡ አየዋለሁ ፡ ፰
በቀኜ ፡ ነውና ፡ አልታወክም ።
ስለዚህ ፡ ልቤን ፡ ደስ ፡ አለው ፡ ፱
አንደበቴም ፡ ሐሤትን ፡ አደረገች ፤
ሥጋዬ ፡ ደግሞ ፡ በተስፋ ፡ ታድራለች ።
ነፍሴን ፡ በሲኦል ፡ አትተዋትምና ፡ ፲
ቅዱስህንም ፡ በመቃብር ፡ አትተወውም ።
የሕይወትን ፡ መንገድ ፡ አሳየኸኝ ፤ ፲፩
በፊትህ ፡ ባለው ፡ ችሮታህ ፡ ደስታን ፡ አጠገብከኝ ፤
በቀኝህም ፡ የዘላለም ፡ ደስታ ፡ አለ ።

መዝሙር ፡ ፲፮ ።

ስ ለ ራ ሱ ።

አቤቱ ፡ ጽድቄን ፡ ተመልከት ፡ ጩኸቴንም ፡ አድምጥ ፡ ፩
ተንኰል ፡ የሌለበት ፡ ጸሎቴን ፡ ተቀበል ።
ፍርዴ ፡ ከፊትህ ፡ ይውጣ ፡ ፪
ዓይኖችህም ፡ በቅንነት ፡ ይመልከቱ ።
ልቤን ፡ ፈተንኸው ፡ በሌሊትም ፡ ጐበኘኸኝ ፤ ፫
ፈተንኸኝ ፡ ምክንያት ፡ አላገኘህብኝም ።
የሰውን ፡ ሥራ ፡ አንደበቴ ፡ እንዳይናገር ፡ ፈቃዴ ፡ ነው ፤ ፬
ስለ ፡ ትእዛዝህ ፡ ቃል ፡ ጥብቅ ፡ የሆኑ ፡ ሕጎችን ፡ ጠበቅሁ ።
እግሮቼ ፡ እንዳይናወጡ ፡ አረማመዴን ፡ በመንገድህ ፡ አጽና ።
አቤቱ ፡ ትሰማኝ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ እጣራለሁ ፤ ፭
ጆሮህን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አዘንብል ፡ ቃሌንም ፡ ስማ ።
የሚያምኑብህን ፡ ከተቃዋሚ ፤ ፮
በክንድህ ፡ የምታድናቸው ፡ ፯
ቸርነትህን ፡ ድንቅ ፡ አድርገህ ፡ ግለጠው ።
ከሚያስጨንቁኝ ፡ ከኃጢአተኞች ፡ ፰
ነፍሴንም ፡ ከሚከቧት ፡ ጠላቶቼ ፡ ሁሉ ፤
እንደ ፡ ዓይን ፡ ብሌን ፡ ጠብቀኝ ፡ ፱
በክንፎችህ ፡ ጥላ ፡ ሰውረኝ ።
እንጀታቸውን ፡ በስብ ፡ ዘጠሩ ፡ ፲
በአፋቸውም ፡ ትዕቢትን ፡ ተናገሩ ።
አሁንም ፡ አረማመዳችንን ፡ ተመለከቱ ፤ ፲፩
ዓይናቸውን ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ዝቅ ፡ ዝቅ ፡ አደረጉ ።
እነርሱ ፡ ንጥቂያን ፡ እንደሚናፍቅ ፡ አንበሳ ፡ ፲፪
ተሸምቆም ፡ እንደሚኖር ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ደቦል ፡ ናቸው ።

፲፫ ተንሥእ ፡ እግዚኦ ፡ ብጽሖሙ ፡ ወአዕቅጾሙ ።
ወባልሓ ፡ እምኩናት ፡ ለነፍስየ ።
ስይፍከ ፡ ላዕለ ፡ ፀረ ፡ እዴከ ።
፲፬ እግዚኦ ፡ እምውኁዳን ፡ ምድር ።
ንፍቆሙ ፡ በሕይወቶሙ ።
እምኅቡአቲከ ፡ ጸግበት ፡ ከርሦሙ ።
ጸግቡ ፡ ደቂቆሙ ፡ ወኃደጉ ፡ ትራፋቲሆሙ ፡
ለሕፃናቲሆሙ ።
፲፭ ወአንሰ ፡ በጽድቅከ ፡ እሬኢ ፡ ገጸከ ።
ወእጸግብ ፡ በርእየ ፡ ስብሐቲከ ።

## መዝሙር ፡ ፲፯ ።

ነገሩ ፡ ለዳዊት ፡ ዘይኃሪ ፡ አመ ፡ ኃልቁ ፡ ጸላእቱ ።

፩ አፈቅረከ ፡ እግዚኦ ፡ በኃይልየ ።
፪ እግዚአብሔር ፡ ኀይልየ ፡ ወፀወንየ ፡ ወመድኃኒየ ።
አምላኪየ ፡ ወረዳኢየ ፡ ወእትዌከል ፡ ቦቱ ።
ምኢመንየ ፡ ወቀርነ ፡ ሕይወትየ ፡ ወምስካይየ ።
፫ እንተ ፡ ሰቡ ፡ ጸዋዕክዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አድኅን ፡ እምጸርየ ።
፬ አኃዙኒ ፡ ጻዕረ ፡ ሞት ።
ወውኂዘ ፡ ዐመፃ ፡ ሆከኒ ።
፭ ዐገቱኒ ፡ ጻዕረ ፡ ሲኦል ።
ወበጽሑኒ ፡ መሣግረ ፡ ሞት ።
፮ ሶበ ፡ ተመንደብኩ ፡ ጸዋዕክዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
ወጸራኅኩ ፡ ኀበ ፡ አምላኪየ ።
ወሰምዐኒ ፡ በጽርሐ ፡ መቅደሱ ፡ ቃልየ ።
ወጽራኅየኒ ፡ ቦአ ፡ ቅድሜሁ ፡ ውስተ ፡ እዘኒሁ ።

፯ ርዕደት ፡ ወአድለቅለቀት ፡ ምድር ።
ወአንቀልቀሉ ፡ መሠረታተ ፡ አድባር ።
ተሀውኩ ፡ እስመ ፡ ተምዖሙ ፡ እግዚአብሔር ።
፰ ዐርገ ፡ ጢስ ፡ እመዓቱ ።
ወነደ ፡ እሳት ፡ እምቅድመ ፡ ገጹ ።
ኀተወ ፡ አፍሓም ፡ እምኔሁ ።
፱ አጽነነ ፡ ሰማያተ ፡ ወወረደ ።
ወቆባር ፡ ታሕተ ፡ እገሪሁ ።
፲ ተጽዕነ ፡ ላዕለ ፡ ኪሩቤል ፡ ወሠረረ ።
ወሠረረ ፡ በክንፈ ፡ ነፋስ ።
፲፩ ወረሰየ ፡ ጽልመተ ፡ ምስዋሮ ።
ወዐውዶሂ ፡ ጽላሎቱ ።
ጸልሙ ፡ ማያት ፡ በውስተ ፡ ደመናት ።
፲፪ ወእምብርሃነ ፡ ገጹ ፡ ኀለፉ ፡ ደመናት ፡ ቅድሜሁ ።
በረድ ፡ ወአፍሓመ ፡ እሳት ።
፲፫ አንጐድጐደ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሰማያት ።
ወልዑል ፡ ወሀበ ፡ ቃሎ ።
፲፬ ፈነወ ፡ አሕፃሁ ፡ ወዘረዎሙ ።
አብዝኀ ፡ መባርቅቲሁ ፡ ወሆኮሙ ።
ወአስተርአዩ ፡ አንቅዕተ ፡ ማያት ።
ወተከሥቱ ፡ መሠረታተ ፡ ዓለም ።
፲፭ እምተግሣጽከ ፡ እግዚኦ ።
ወእምእስትንፋሰ ፡ መንፈሰ ፡ መዓትከ ።
፲፮ ፈነወ ፡ እምአርያም ፡ ወነሥአኒ ።
ወተመጠወኒ ፡ እማይ ፡ ብዙኅ ።
፲፯ ወአድኀነኒ ፡ እምፀርየ ፡ ጽኑዓን ።
ወእምጸላእትየ ፡ እስመ ፡ ይኄይሉኒ ።
፲፰ ወበጽሑኒ ፡ በዕለተ ፡ ምንዳቤየ ።
ወኮነኒ ፡ እግዚአብሔር ፡ ምስካይየ ።



እቤቱ ፡ ተነሥ ፤ ቀድመህም፡ወደታች፡ጣላቸው ፤ ፲፫
ነፍሴን ፡ ከኃጢአተኛ ፡ በሰይፍህ ፡ አድናት ።
አቤቱ፡ዕድል፡ፈንታቸው፡ በሕይወታቸው ፡ ከሆኑት ፤ ፲፬
ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ሰዎች፡ በእጅህ ፡ አድነኝ ።
ከሰወርኸው ፡ መዝገብህ ፡ ሆዳቸውን ፡ አጠገብህ ፡
ልጆቻቸው ፡ ብዙ ፡ ናቸው ፤
የተረፋቸውንም ፡ ለሕፃናቶቻቸው ፡ ያተርፋሉ ።
እኔ ፡ ግን ፡ በጽድቅ ፡ ፊትህን ፡ አያለሁ ፤ ፲፭
ክብርህንም ፡ አየሁ ፡ እጠግባለሁ ።

## መዝሙር ፡ ፲፯ ።

ከሳኦልና ፡ ከጠላቶቹ ፡ ሁሉ ፡ እጅ ፡ ስለመዳኑ የእግዚአብሔር ፡
አገልጋይ ፡ የዳዊት ፡ መዝሙር ።

አቤቱ ፡ ኃይ፡ መከታዬ ፡ ሆይ ፡ እወድሃለሁ ። ፩
እግዚአብሔር ፡ ኃይሌ ፡ አምባዬ ፡ መድኃኒቴ ፡ ፪
አምላኬ ፡ በእርሱም ፡ የምተማመንበት ፡ ረዳቴ ፡
መታመኛዬና፡የደኅንነቴ ፡ መገኛ፡መጠጊያዬም ፡ ነው ።
ምስጋና ፡ የሚገባውን ፡ እግዚአብሔርን ፡ እጠራለሁ ፡ ፫
ከጠላቶቼም ፡ እድናለሁ ።
የሞት ፡ ጣር ፡ ያዘኝ ፡ ፬
የዓመፅ ፡ ፈሳሽም ፡ አስፈራኝ ።
የሲኦል ፡ ጣር ፡ ከበበኝ ፤ ፭
የሞት ፡ ወጥመድም ፡ አጠመደኝ ።
በጨነቀኝ ፡ ጊዜ ፡ እግዚብሔርን ፡ ጠራሁት ፡ ፮
ወደ ፡ አምላኬም ፡ ጮኽሁ ፤
ከመቅደሱም ፡ ቃሌን ፡ ሰማኝ ፡
ጩኸቴም ፡ በፊቱ ፡ ወደ ፡ ጆሮው ፡ ገባ ።

ምድርም ፡ ተቀንጠቀጠች ፡ ተናወጠችም ፡ ፯
የተራሮችም ፡ መሠረቶች ፡ ተነቃነቁ ፤
እግዚአብሔርም ፡ ተቆጥቶአልና ፡ ተንቀጠቀጡ ።
ከቍጣው፡ጢስ፡ጤሰ፡ከፊቱም፡የሚያቃጥል፡እሳት፡ነደደ ፰
ፍምም ፡ ከእርሱ ፡ ወጣ ።
ሰማዮችን ፡ ዝቅ ፡ አደረገ ፡ ወረደም ፡ ፱
ጨለማ ፡ ከእግሩ ፡ በታች ፡ ነበረ ።
በኪሩቤልም ፡ ላይ ፡ ተቀምጦ ፡ ለመብረር ፡ ተፋጠነ ፤ ፲
በነፋስም ፡ ክንፍ ፡ በረረ ።
መሰወሪያውን ፡ ጨለማ ፡ አደረገ ፤ ፲፩
በዙሪያውም ፡ የነበረው ፡ ድንኳን ፤
በደመናት ፡ ውስጥ ፡ የጨለማ ፡ ውኃ ፡ ነበረ ።
በፊቱ ፡ካለው ፡ ብርሃን ፡ የተነሣ ፡ ደመናትና ፡ በረዶ ፤ ፲፪
የእሳቱም ፡ ነበልባል ፡ በፊቱ ፡ አለፉ ።
እግዚአብሔርም ከሰማያት ፡ አንጐደጐደ ፡ ፲፫
ልዑልም ፡ ቃሉን ፡ ሰጠ ።
ፍላጻውን ፡ ላከ ፡ በተናቸውም ፤ ፲፬
መብረቆችን ፡ አበዛ ፡ አወካቸውም ።
አቤቱ ፡ ከዘለፋህ ፡ ፲፭
ከመዓትህም ፡ መንፈስ ፡ እስተንፋስ ፡ የተነሣ ፤
የውኆች ፡ ምንጮች ፡ ታዩ ፡
የዓለም ፡ መሠረቶችም ፡ ተገለጡ ።
ከላይ ፡ ኃይል ፡ ልኮ ፡ ወሰደኝ ፡ ፲፮
ከብዙ ፡ ውኆምች ፡ አወጣኝ ።
ብርቱዎች ፡ ጠላቶቼ ፡ ከሚጠሉኝም ፡ አዳነኝ ፤ ፲፯
በርትተውብኝ ፡ ነበርና ።
በመከራዬ ፡ ቀን ፡ ደረሱብኝ ፡ ፲፰
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ደገፋዬ ፡ ሆነ ።

፲፱ ወአውዐአኒ ፡ ውስተ ፡ መርኅብ ።
ወአድኀነኒ ፡ እስመ ፡ ይፈቅደኒ ።
፳ የዐስየኒ ፡ እግዚአብሔር ፡ በከመ ፡ ጽድቅየ ።
ወይፈድየኒ ፡ በከመ ፡ ንጽሐ ፡ እደውየ ።
፳፩ እስመ ፡ ዐቀብኩ ፡ ፍናዊሁ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
ወኢአበስኩ ፡ ለአምላኪየ ።
፳፪ እስመ ፡ ኵሉ ፡ ኵነኔሁ ፡ ቅድሜየ ፡ ውእቱ ።
ወጽድቁኒ ፡ ኢርኅቀ ፡ እምኔየ ።
፳፫ ወእከውን ፡ ንጹሐ ፡ ምስሌሁ ።
ወእትዐቀብ ፡ እምኀጢአትየ ።
፳፬ የዐስየኒ ፡ እግዚአብሔር ፡ በከመ ፡ ጽድቅየ ።
ወይፈድየኒ ፡ በከመ ፡ ንጽሐ ፡ እደውየ ።
በቅድመ ፡ አዕይንቲሁ ።
፳፭ ምስለ ፡ ጻድቅ ፡ ትጸድቅ ።
ወምስለ ፡ ብእሲ ፡ ንጹሕ ፡ ንጹሐ ፡ ትከውን ።
፳፮ ወምስለ ፡ ኅሩይ ፡ ኅሩየ ፡ ትከውን ።
ወምስለ ፡ ጠዋይ ፡ ትጠዊ ።
፳፯ እስመ ፡ አንተ ፡ እግዚኦ ፡ ታድኅኖ ፡ ለሕዝብ ፡ ትሑት
ወታኀስሮሙ ፡ ለአዕይንተ ፡ ዕቡያን ።
፳፰ እስመ ፡ አንተ ፡ ታበርህ ፡ ማኅቶትየ ፡ እግዚኦ ።
አምላኪየ ፡ ያበርህ ፡ ጽልመትየ ።
፳፱ እስመ ፡ ብከ ፡ እድኅን ፡ እመንሱት ።
ወበአምላኪየ ፡ እትዐደዋ ፡ ለዐረፍት ።
፴ ለአምላኪየሰ ፡ ንጹሕ ፡ ፍኖቱ ።
ቃለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ርሱን ።
ወምእመኖሙ፡ውእቱ ፡ ለኵሎሙ፡እለ፡ይትዌ ከሉ፡ቦቱ
፴፩ መኑ ፡ ውእቱ ፡ አምላክ ፡ ዘእንበለ ፡ እግዚአብሔር ፡
ወመኑ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዘእንበለ ፡ አምላክነ ።
፴፪ እግዚአብሔር ፡ ዘያቀንተኒ ፡ ኀይለ ።
ወረሰየ ፡ ንጹሐ ፡ ለፍኖትየ ።
፴፫ ዘያረትዖን ፡ ከመ ፡ ኀየል ፡ ለእገርየ ።
ወያቀውመኒ ፡ ውስተ ፡ መልዕልት ።
፴፬ ዘይሜህሮን ፡ ጸብአ ፡ ለእደውየ ።
ወረሰየ ፡ ቀስተ ፡ ብርት ፡ ለመዝራዕትየ ።
፴፭ ወወሀብከኒ ፡ ምእመነ ፡ ለመድኀኒትየ ።
ወየማንከ ፡ ተወክፈኒ ።
ወትምህርትከ ፡ ዘያጸንዐኒ ፡ ለዝልፉ ።
ወተግሣጽከ ፡ ውእቱ ፡ ዘይሜህረኒ ።
፴፮ ወአርኃብከ ፡ መከየድየ ፡ በመትሕቴየ ።
ወኢደክመ ፡ ሰኰናየ ።
፴፯ እዴግኖሙ ፡ ለፀርየ ፡ ወእእኅዞሙ ።
ወኢይትመየጥ ፡ እስከ ፡ አጠፍኦሙ ።
፴፰ አመንድቦሙ ፡ ወኢይክሉ ፡ ቀዊመ ።
ወይወድቁ ፡ ታሕተ ፡ እገርየ ።
፴፱ ወታቀንተኒ ፡ ኃይለ ፡ በጸብእ ።
ወአዕቀጽኮሙ ፡ ለኵሎሙ ፡ እለ ፡ ቆሙ ፡
ላዕሌየ ፡ በመትሕቴየ ።
፵ ወመጠውከኒ ፡ ዘባኖሙ ፡ ለፀርየ ።
ወሰረውኮሙ ፡ ለጸላእትየ ።
፵፩ አውየዉ ፡ ወኀጥኡ ፡ ዘይረድኦሙ ።
ወኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡ ኢሰምዖሙ ።
፵፪ አሐርጾሙ ፡ ከመ ፡ ጸበል ፡ ዘቅድመ ፡ ገጸ ፡ ነፋስ ።
ወእከይዶሙ ፡ ከመ ፡ ጽንጕነ ፡ መርሕብ ።
፵፫ አድኅነኒ ፡ እምነቢበ ፡ አሕዛብ ።
ወትሠይመኒ ፡ ውስተ ፡ ርእሰ ፡ ሕዝብ ።
ሕዝብ ፡ ዘኢየአምር ፡ ተቀንየ ፡ ሊተ ።
፵፬ ውስተ ፡ ምስማዐ ፡ እዝን ፡ ተሰጥዉኒ ።
ውሉደ ፡ ነኪር ፡ ሐሰዉኒ ።
፵፭ ውሉደ ፡ ነኪር ፡ በልዩ ።
ወሐንከሱ ፡ በፍኖቶሙ ።



ወደ ፡ ሰፊ ፡ ስፍራም ፡ አወጣኝ ፤ ፲፱
ወዶኛልና ፡ አዳነኝ ።
እግዚአብሔር ፡እንደ ፡ ጽድቄ ፡ ይከፍለኛል ፡ ፳
እንደ ፡ እጄም ፡ ንጽሕና ፡ ይመልስልኛል ።
የእግዚአብሔርን መንገድ ፡ ጠብቄአለሁና ፤ ፳፩
በአምላኬም ፡ አላመፅሁም ።
ፍርዱ ፡ ሁሉ ፡ በፊቴ ፡ ነበረና ፤ ፳፪
ሥርዓቱንም ፡ ከፊቴ ፡ አላራቅሁም ።
በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ቅን ፡ ነበርሁ ፤ ፳፫
ከኃጢአቴም ፡ ተጠበቅሁ ።
ስለዚህ ፡እግዚአብሔርእንደ ፡ ጽድቄ ፡ እንደ ፡ እጄም ፳፬
ንጽሕና ፡ በዓይኖቹ ፡ ፊት ፡ መለሰልኝ ።
ከቸር ፡ ሰው ፡ ጋር ፡ ቸር ፡ ሆነህ ፡ ትገኛለህ ፤ ፳፭
ከቅን ፡ ሰው ፡ ጋር ፡ ቅን ፡ ሆነህ ፡ ትገኛለህ ።
ከንጹሕ ፡ ጋር ፡ ንጹሕ ፡ ሆነህ ፡ ትገኛለህ ፤ ፳፮
ከጠማማም ፡ ጋር ፡ ጠማማ ፡ ሆነህ ፡ ትገኛለህ ።
አንተ ፡ የተጠቃውን ፡ ሕዝብ ፡ ታድናለህና ፡ ፳፯
የትዕቢተኞችን ፡ ዓይን ፡ ግን ፡ ታዋርዳለህ ።
አንተ ፡ መብራቴን ፡ ታበራለህና ፤ ፳፰
እግዚአብሔር አምላኬ ፡ ጨለማዬን ፡ ያበራል ።
በአንተ ፡ ከጥፋት ፡ እድናለሁና ፤ ፳፱
በአምላኬም ፡ ቅጥሩን ፡ እዘላለሁ ።
የአምላኬ ፡ መንገድ ፡ ፍጹም ፡ ነው ፤ ፴
የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ የነጠረ ፡ ነው ፤
በእርሱ ፡ ለሚታመኑት ፡ ሁሉ ፡ ጋሻ ፡ ነው ።
ከእግዚአብሔር ፡በቀር ፡ አምላክ ፡ ማን ፡ አለ ? ፴፩
ከአምላካችን ፡ በቀር ፡ አምላክ ፡ ማን ፡ ነው ። ?
ኃይልን ፡ የሚያስታጥቀኝ ፡ መንገዴንም ፡ የሚያቃና ፤ ፴፪
እግሮቼን ፡ እንደ ፡ ብሖር ፡ እግሮች ፡ የሚያቀላጥፍ ፤ ፴፫
በኮረብቶችም ፡ የሚያቆመኝ ፡ እሱ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነውና ።
እጆቼን ፡ ሰልፍ ፡ ያስተምራል ፤ ፴፬
በክንዴም ፡ የናስ ፡ ቀስት ፡ አነጣጥራሁ ።
ለደኅንነቴም ፡ መታመኛን ፡ ሰጠኸኝ ፡ ፴፭
ቀኝህም ፡ ትረዳኛለች ፡
ትምህርትህም ፡ ለዘላለም ፡ ታጽናናኛለች ፤
ተግሣጽህም ፡ ታስተምረኛለች ።
አረማመዴን ፡ አስተካከልህ ፤ ፴፮
እግሮቼም ፡ አልተንሸራተቱም ።
ጠላቶቼን ፡ አሳድዳቸዋለሁ ፡ እይዛቸውማለሁ ፤ ፴፯
እስካጠፋቸውም ፡ ድረስ ፡ አልመለስም ።
አስጨንቃቸዋለሁ ፡ መቆምም ፡ አይችሉም ፡ ፴፰
ከእግሬም ፡ በታች ፡ ይወድቃሉ ።
ለሰልፍም ፡ ኃይልን ፡ ታስታጥቀኛለህ ፤ ፴፱
በበላዬ ፡ የቆሙትን ፡ ሁሉ ፡
በበታቼ ፡ ታስገዛቸዋለህ ።
የጠላቶቼን ፡ ጀርባ ፡ ሰጠኸኝ ፡ ፵
የሚጠሉኝንም ፡ አጠፋኻቸው ።
ጮኹ ፡ የሚረዳቸውም ፡ አልተገኘም ፡ ፵፩
ወደ ፡እግዚአብሔርም ፡ ጮኹ ፡ አልሰማቸውም ።
እንደ ፡ ትቢያ ፡ በነፋስ ፡ ፊት ፡ እበትናቸዋለሁ ፡ ፵፪
እንደ ፡ ጭቃም ፡ እረግጣቸዋለሁ ።
ከሕዝብ ፡ ክርክር ፡ ታድነኛለህ ፡ ፵፫
የአሕዛብም ፡ ራስ ፡ አድርገህ ፡ ትሾመኛለህ ።
የማላውቀው ፡ ሕዝብም ፡ ይገዛልኛል ።
በጆሮ ፡ ሰምተው ፡ ተገዙልኝ ፤ ፵፬
የልዩ ፡ ልዩ ፡ ወገኖች ፡ ደለሉኝ ።
የባዕድ ፡ ልጆች ፡ ደከሙ ፡ ፵፭
በመንገዳቸውም ፡ ተሰናከሉ ።

፵፮ ሕያው ፡ እግዚአብሔር ፡ ወቡሩክ ፡ አምላኪየ ።
ወተለዐለ ፡ አምላከ ፡ መድኃኒትየ ።
አምላኪየ ፡ ያገብእ ፡ በቀልየ ።
፵፯ ወአግረረ ፡ ሊተ ፡ አሕዛበ ፡ በመትሕቴየ ።
፵፰ ዘያባልሐኒ ፡ እምጸላእትየ ፡ ምንስዋን ።
ወዘያሌዕለኒ ፡ እምእለ ፡ ቆሙ ፡ ላዕሌየ ።
እምብእሲ ፡ ገፋዒ ፡ ባልሐኒ ።
፵፱ በእንተዝ ፡ እገኒ ፡ ለከ ፡ በውስተ ፡ አሕዛብ ፡ እግዚኦ ።
ወእዜምር ፡ ለስምከ ።
፶ ዘያዐብዮ ፡ ለመድኃኒተ ፡ ንጉሥ ።
ወይገብር ፡ ምሕረቶ ፡ ለመሢሒሁ ።
ለዳዊት ፡ ወለዘርዑ ፡ እስከ ፡ ለዓለም ።

መዝሙር ፡ ፲፰ ።

በእንተ ፡ ሥነ ፡ ፍጥረት ።

፩ ሰማያት ፡ ይነግራ ፡ ስብሐተ ፡ እግዚአብሔር ።
ወግብረ ፡ እደዊሁ ፡ ያየድዓ ፡ ሰማያት ።
፪ ዕለት ፡ ለዕለት ፡ ትጐሥዕ ፡ ነቢበ ።
ወሌሊት ፡ ለሌሊት ፡ ታየድዕ ፡ ጥበበ ።
፫ አልቦ ፡ ነገር ፡ ወአልቦ ፡ ነቢብ ፡ ዘኢተሰምዐ ፡ ቃሎሙ
፬ ውስተ ፡ ኵሉ ፡ ምድር ፡ ወፅአ ፡ ነገሮሙ ።
ወእስከ ፡ አጽናፈ ፡ ዓለም ፡ በጽሐ ፡ ነቢቦሙ ።
፭ ወውስተ ፡ ፀሐይ ፡ ሤመ ፡ ጽላሎቶ ።
ወውእቱሰ ፡ ከመ ፡ መርዓዊ ፡ ዘይወፅእ ፡ እምጽርሑ
ይትፌሣሕ ፡ ከመ ፡ ያርብሕ ፡ ዘይሜርድ ፡ ፍኖቶ
፮ እምአጽናፈ ፡ ሰማይ ፡ ሙፃኡ ።
ወእስከ ፡ አጽናፈ ፡ ዓለም ፡ ምእታዊ ።
አልቦ ፡ ዘይትኀባእ ፡ እምላህቡ ።

፯ ሕገ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ንጹሕ ፡ ወይመይጣ ፡ ለነፍስ
ስምዑ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እሙን ፡ ወያጠብብ ፡
ሕፃናተ ።
፰ ኵነኔሁ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ርቱዕ ፡ ወያስተፌሥሕ ፡ ልበ ።
ትእዛዙ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ብሩህ ፡ ወያበርህ ፡ አዕይንተ ።
፱ ፈሪሀ ፡ እግዚአብሔር ፡ ንጹሕ ፡ ወየሐዩ ፡ ለዓለም ።
ፍትሑ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ጽድቅ ፡ ወርቱዕ ፡ ኅቡረ ።
፲ ወይትፌቶ ፡ እምወርቅ ፡ ወእምዕንቍ ፡ ክቡር ።
ወይጥዕም ፡ እመዓር ፡ ወሦከር ።
፲፩ ወገብርከሰ ፡ የዐቅቦ ።
ወበዐቂቦቱ ፡ ይትዐሰይ ፡ ብዙኀ ።
፲፪ ስሒተ ፡ መኑ ፡ ይሌብዋ ።
እምኅቡአትየ ፡ አንጽሐኒ ።
፲፫ ወእምነኪር ፡ መሐኮ ፡ ለገብርከ ።
እመሰ ፡ ኢቀነዩኒ ፡ ውእተ ፡ ጊዜ ፡ ንጹሐ ፡ እከውን ።
ወእነጽሕ ፡ እምዐባይ ፡ ኃጢአትየ ።
ወይከውን ፡ ሥሙረ ፡ ቃለ ፡ አፉየ ።
ወኅሊና ፡ ልብየኒ ፡ ቅድሜየ ፡ ውእቱ ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ።
፲፬ እግዚኦ ፡ ረዳኢየ ፡ ወመድኅንየ ።

መዝሙር ፡ ፲፱ ።

በእንተ ፡ ሕዝቅያስ ።

፩ ይስማዕከ ፡ እግዚአብሔር ፡ በዕለተ ፡ ምንዳቤከ ።
ወይቁም ፡ ለከ ፡ ስሙ ፡ ለአምላከ ፡ ያዕቆብ ።
፪ ወይፈኑ ፡ ለከ ፡ ረድኤተ ፡ እመቅደሱ ።
ወእምጽዮን ፡ ይትወከፍከ ።



እግዚአብሔር ፡ ሕያው፡ነው፡አምላኬም፡ቡሩክ፡ነው፡ ፵፮
በቀሌን ፡ የሚመልስልኝ ፡ አምላክ ፡
የመድኃኒቴም ፡ አምላክ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይበል ፡
አሕዛብን ፡ በበታቼ ፡ ያስገዛልኛል ። ፵፯
ከጠላቶቼ ፡ የሚታደገኝ ፡ እርሱ ፡ ነው ፤ ፵፰
በእኔም፡ላይ፡ ከቆሙ፡ ይልቅ፡ ከፍ ፡ ከፍ፡ ታደርገኛለህ፡
ከግፈኛ ፡ ሰው ፡ ታድነኛለህ ።
አቤቱ ፡ ስለዚህ ፡ በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ አመሰግንሃለሁ ፡
ለስምህም ፡ እዘምራለሁ ።
የንጉሡን ፡ መድኃኒት ፡ ለታላቅ ፡ ያደርጋል ። ፵፱
ቸርነቱንም ፡ ለቀባው ፤ ለዳዊትና ፡ ለዘሩ ፡ ፶
ለዘላለም ፡ ይሰጣል ።

መዝሙር ፡ ፲፰ ።

ስለ ፡ ሥነ ፡ ፍጥረት ።

ሰማያት ፡ የእግዚአብሔርን ክብር ፡ ይናገራሉ ፡ ፩
የሰማይም ፤ ጠፈር ፡ የእጁን ፡ ሥራ ፡ ያወራል ።
ቀኒቱ ፡ ለቀን ፡ ነገርን ፡ ታወጣለች ፡ ፪
ሌሊትም ፡ ለሌሊት ፡ እውቀትን ፡ ትናገራለች ።
ነገር ፡ የለም ፡ መናገርም ፡ የለም ፡ ፫
ድምፃቸውም ፡ አይሰማም ።
ድምፃቸው ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ተሰማ ፡ ፬
ቃላቸውም ፡ ሁሉ፡ እስከ ፡ ዓለም ፡ ዳርቻ ፡ ወጣ ።
በእነርሱም ፡ ውስጥ ፡ የፀሐይን ፡ ድንኳን ፡ አደረገ ፤ ፭
እርሱም ፡ እንደ ፡ ሙሽራ ፡ ከእልፍኙ ፡ ይወጣል ፤
እንደ ፡ አርበኛ ፡ በመንገዱ ፡ ለመሮጥ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ።
አወጣጡ ፡ ከሰማያት ፡ ዳርቻ ፡ ነው ፡ ፮
ሂደቱም ፡ እስከ ፡ ዳርቻቸው ፡ ነው ፤
ከዋዕይነቱም ፡ የሚሰወር ፡ የለም ።

የእግዚአብሔር ፡ሕግ፡ ፍጹም፡ ነው ፡ነፍስን፡ይመልሳል፤
የእግዚአብሔር ፡ምስክር ፡ የታመነ ፡ ነው ፤ ሕፃናትን ፡
አዋቂዎች ፡ ያደርጋል ።
እግዚአብሔር ፡ ሥርዓት ፡ ቅን ፡ ነው ፡ ልብን ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ፡
የእግዚአብሔር ፡ ትእዛዝ ፡ ብሩህ ፡ ነው ፡ ዐይንንም ፡ ያበራል ።
የእግዚአብሔርን፡ መፍራት፡ ንጹሕነት ፡ ነው ፤ ለዘለዓለ ፡ ያኖራል ፡
የእግዚአብሔር ፡ ፍርድ ፡ እውነትና ፡ ቅንነት ፡ በአንድነት ፡ ነው ።

ከወርቅና ፡ ከክቡር ፡ ዕንቍ ፡ ይልቅ ፡ ይወደዳል ፤ ፲
ከማርና ፡ ከማር ፡ ወለላም ፡ ይጣፍጣል ።
ባሪያህ ፡ ደግሞ ፡ ይጠብቀዋል ፤ ፲፩
በመጠበቁም ፡ እጅግ ፡ ይጠቀማል ።
ስሕተትን ፡ ማን ፡ ያስታውሳታል ? ፲፪
ከተሰወረ ፡ ኃጢአት ፡ አንጻኝ ።
የድፍረት፡ ኃጢአት፡እንዳይገዛኝ ፡ ባሪያህን ፡ ጠብቅ ፤ ፲፫
የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ፍጹም ፡ እሆናለሁ ፡
ከታላቁም ፡ ኃጢአት ፡ እነፃለሁ ።
አቤቱ ፡ ረድኤቴ ፡ መድኃኒቴም ፡ ፲፬
የአፌ ፡ አነጋገር ፡ የልቤም ፡ አሳብ ፤
በፊትህ ፡ ያማረ ፡ የተወደደ ፡ ይሁን ።

መዝሙር ፡ ፲፱ ።

ስለ ሕዝቅያስ ።

በመከራህ ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ ይስማህ ። ፩
የያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ ስም ፡ አጽንቶ ፡ ያቁምህ ።
ከመቅደሱ ፡ ረዳትን ፡ ይላክልህ ፤ ፪
ከጽዮንም ፡ ድጋፍ ፡ ይስጥህ ።

፫ ወይዝክር ፡ ለከ ፡ ኵሎ ፡ መሥዋዕተከ ።
ወይጥልል ፡ ለከ ፡ ቍርባነከ ።
፬ የሀብከ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዘከመ ፡ ልብከ ።
ወይፈጽም ፡ ለከ ፡ ኵሎ ፡ ምምረተከ ።
፭ ወንትፌሣሕ ፡ በአድኅኖትከ ።
ወንዐቢ ፡ በስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክነ ።
ወይፈጽም ፡ ለከ ፡ እግዚአብሔር ፡ ኵሎ ፡ ስእለተከ ።
፮ ይእዜ ፡ አእመርኩ ፡ ከመ ፡ አድኃኖ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለመሢሑ ።
ወይሰጠዎ ፡ እምሰማይ ፡ መቅደሱ ።
በኃይለ ፡ አድኅኖተ ፡ የማኑ ።
፯ እሙንቱሰ ፡ በአፍራስ ፡ ወበሠረገላት ።
ወንሕነሰ ፡ ነዐቢ ፡ በስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክነ።
፰ እሙንቱሰ ፡ ተዐቅጹ ፡ ወወድቁ ።
ወንሕነሰ ፡ ተንሣእነ ፡ ወረታዕነ ።
፱ እግዚኦ ፡ አድኅኖ ፡ ለንጉሥ ።
ወስምዐነ ፡ በዕለተ ፡ ንጼውዐከ ።

መዝሙር ፡ ፳ ።

በእንተ ፡ ሕዝቅያስ ።

፩ እግዚኦ ፡ በኀይልከ ፡ ይትፌሣሕ ፡ ንጉሥ ።
ወብዙኀ ፡ ይትሐሠይ ፡ በአድኅኖትከ ።
፪ ፍትወተ ፡ ነፍሱ ፡ ወሀብኮ ።
ወስእለተ ፡ ከናፍሪሁ ፡ ኢከላእኮ ።
፫ እስመ ፡ በጸሕኮ ፡ በበረከት ፡ ሠናይ ።
ወአንበርከ ፡ አክሊለ ፡ ዲበ ፡ ርእሱ ፡ ዘእምዕንቍ ፡ ክቡር ።
፬ ሐዩወ ፡ ሰአለከ ፡ ወሀብኮ ።
ለነዋህ ፡ መዋዕል ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ።
፭ ዐቢይ ፡ ክብሩ ፡ በአድኅኖትከ ።
ክብረ ፡ ወስብሐተ ፡ ወሰከ ።
፮ እስመ ፡ ወሀብኮ ፡ በረከተ ፡ ዘለዓለመ ፡ ዓለም ።
ወታስተፌሥሖ ፡ በሐሤተ ፡ ገጽከ ።
፯ እስመ ፡ ተወከለ ፡ ንጉሥ ፡ በእግዚአብሔር ።
ወኢይትሐወክ ፡ በምሕረቱ ፡ ለልዑል ።
፰ ትርከቦሙ ፡ እዴከ ፡ ለኵሎሙ ፡ ፀርከ ።
ወትትራከቦሙ ፡ እዴከ ፡ ለኵሎሙ ፡ ጸላእትከ ።
፱ ወትረስዮሙ ፡ ከመ ፡ እቶነ ፡ እሳት ፡ ለጊዜ ፡ ገጽከ ።
እግዚኦ ፡ በመዓትከ ፡ ሁኮሙ ፡ ወትብልዖሙ ፡ እሳት።
፲ ወፍሬሆሙኒ ፡ ሰዐር ፡ እምድር ።
ወዘርዖሙኒ ፡ እምዕጓለ ፡ እመሕያው ።
፲፩ እስመ ፡ ሚጥዋ ፡ ለዐመፃ ፡ ላዕሌከ ።
ወሐለዩ ፡ ምክረ ፡ እንተ ፡ ኢይክሉ ፡ ዐቅሞ ።
፲፪ ወታገብኦሙ ፡ ድኅሬሆሙ ።
ወታስተዴሉ ፡ ገጾሙ ፡ ለጊዜ ፡ መዓትከ ።
፲፫ ተለዐልከ ፡ እግዚኦ ፡ በኀይልከ ።
ንሴብሕ ፡ ወንዜምር ፡ ለጽንዕከ ።



ቍርባንህን ፡ ሁሉ ፡ ያስብልህ ፤ ፫
ቍርባንህን ፡ መሥዋዕትህን ፡ ያለምልምልህ ።
እንደ ፡ ልብህ ፡ ፈቃድ ፡ ይስጥህ ፡ ፬
ፈቃድህንም ፡ ሁሉ ፡ ይፈጽምልህ ።
በማዳንህ ፡ ደስ ፡ ይለናል ፤ ፭
በአምላካችን ፡ ስም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ እንላለን ።
ልመናህን ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይፈጽምልህ ።
እግዚአብሔር ፡ የቀባውን፡ እንዳዳነው ፡ ዛሬ ፡ አወቅሁ ፮
በቀኙ ፡ የማዳኑን ፡ ኃይል ፡ ከሰማይ ፡ የመቅደሱ ፡
አዳራሽ ፡ ይልክለታል ።
እነዚያ ፡ በሠረገላ ፡ እነዚህም ፡ በፈረስ ፡ ይታመናሉ ፡ ፯
እኛ ፡ ግን ፡ በአምላካችን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡
ከፍ ፡ ከፍ ፡ እንላለን ።
እነርሱ ፡ ተሰነካክለው ፡ ወደቁ ፤ ፰
እኛ ፡ ግን ፡ ተነሣን ፡ ጸንተንም ፡ ቆምን ።
አቤቱ ፡ ንጉሥን ፡ አድነው ፡ ፱
በጠራንህም ፡ ቀን ፡ ስማን ።

መዝሙር ፡ ፳ ።

ስለ ሕዝቅያስ ።

አቤቱ ፡ በኃይልህ ፡ ንጉሥ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፤ ፩
በማዳንህ ፡ እጅግ ፡ ሐሤትን ፡ ያደርጋል ።
የልቡን ፡ ፈቃድ ፡ ሰጠኸው ፤ ፪
የከንፈሩንም ፡ ልመና ፡ አልከለከልኸውም ።
በበጎ ፡ በረከት ፡ ደርሰህለታልና ፤ ፫
ክቡር፡ የሆነ፡ የዕንቍ ፡ ዘውድን፡ በራሱ፡ላይ፡አቀዳጀኸው ፬
ሕይወትን፡ ለመነህ፡ለረጅም፡ዘመን፡ሰጠኸው፡ለዘላለሙ ።
በማዳንህ ፡ ክብሩ ፡ ታላቅ ፡ ነው ፤ ፭
ክብርንና ፡ ምስጋናን ፡ ጨመርህለት ።
የዘላለም ፡ በረከትን ፡ ሰጥተኸዋልና ፡ ፮
በፊትህም ፡ ደስታ ፡ ደስ ፡ ታሰኘዋለህ ።
ንጉሥ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ተማምኖአልና ፡ ፯
በልዑልም ፡ ምሕረት ፡ አይናወጥም ።
እጅህ ፡ በጠላቶችህ ፡ ላይ ፡ ትውደቅባቸው ፡ ፰
ቀኝህም ፡ የሚጠሉህን ፡ ሁሉ ፡ ታግኛቸው ።
በተቆጣህም ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ እሳት፡እቶን ፡ ታደርጋቸው ። ፱
እግዚአብሔር ፡ በቍጣው ፡ ያጠፋቸዋል ፡ ፲
እሳትም ፡ ትበላቸዋለች ።
ፍሬአቸውን ፡ ከምድር ፡ ዘራቸውንም ፡ ከሰው ፡
ልጆች ፡ ወገን ፡ ታጠፋለህ ።
ክፋትን ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ ዘርግተዋልና ፡ ፲፩
የማይቻላቸውንም ፡ ምክር ፡ አሰቡ ።
ወደ ፡ ኋላቸው ፡ ትመልሳቸዋለህ ፤ ፲፪
ፍላጻን ፡ በፊታቸው ፡ ላይ ፡ ታዘጋጃለህ ።
አቤቱ ፡ በኃይልህ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ በል ፤ ፲፫
ጽናትህንም ፡ እናመሰግናለን ፡ እንዘምርማለን ።

መዝሙር ፡ ፳፩ ።

በእንተ ፡ ክርስቶስ ፡ ወበእንተ ፡ ርእሱ ።

፩ አምላኪየ ፡ አምላኪየ ፡ ነጽረኒ ፡ ወለምንት ፡ ኀደገኒ ።
ርኁቅ ፡ እምአድኅኖትየ ፡ ቃለ ፡ ኀጢአትየ ።
፪ አምላኪየ ፡ ጸራኅኩ ፡ ኀቤከ ፡ ዕለትየ ፡ ወኢሰማዕከኒ ።
ወሌሊትየኒ ፡ ቅድሜከ ፡ ወኢሐለይከኒ ።

መዝሙር ፡ ፳፩ ።

ስለክርስቶስና ፡ ስለራሱ ።

አምላኬ ፡ አምላኬ ፡ ለምን ፡ ተውኸኝ ? ፩
እኔን ፡ ከማዳንና ፡ የጩኸቴንም ፡ ቃል ፡
ከመስማት ፡ ርቀሃልና ።
አምላኬ ፡ በቀን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ እጠራለሁ ፡ አልመለስህልኝም ፡ ፪
በሌሊትም ፡ እንኳ ፡ ዕረፍት ፡ የለኝም ።

፫ አንተሰ፡ውስተ ፡ ቅዱሳኒከ፡ተኀድር ፡ ስቡሐ፡ እስራኤል
፬ ኪያከ ፡ ተወከሉ ፡ አበዊነ ።
ተወከሉከኒ ፡ ወአድኅንኮሙ ።
፭ ኀቤከ ፡ ጸርኁ ፡ ወድኅኑ ።
ኪያከ ፡ ተወከሉ ፡ ወኢተኀፍሩ ።
፮ አንሰ ፡ ዕፄ ፡ ወአኮ ፡ ሰብእ ።
ምኑን ፡ በኀበ ፡ ሰብእ ፡ ወትሑት ፡ በውስተ ፡ ሕዝብ ።
፯ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይሬእዩኒ ፡ ይትቃጸቡኒ ።
ይብሉ ፡ በከናፍሪሆሙ ፡ ወየሐውሱ ፡ ርእሶሙ ።
፰ ተወከለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለያድኅኖ ።
ወያድኅኖ ፡ እመ ፡ ያፈቅዶ ።
፱ እስመ ፡ አንተ ፡ አውፃእከኒ ፡ እምከርሥ ።
ወተወከልኩከ ፡ እንዘ ፡ ሀሎኩ ፡ ውስተ ፡
አጥባተ ፡ እምየ ።
፲ ላዕሌከ ፡ ተገደፍኩ ፡ እማኅፀን ።
እምከርሠ ፡ እምየ ፡ አንተ ፡ አምላኪየ ።
፲፩ ኢትርኃቅ ፡ እምኔየ ፡ እስመ ፡ አልጸቀ ፡ እትመንደብ ።
እስመ ፡ አልቦ ፡ ዘይረድአኒ ።
፲፪ ዐገቱኒ ፡ አልሕምት ፡ ብዙኃን ።
ወአኃዙኒ ፡ አስዋር ፡ ስቡሓን ።
፲፫ ወአብቀዉ ፡ አፉሆሙ ፡ ላዕሌየ ።
ከመ ፡ አንበሳ ፡ ዘጽኑሕ ፡ ለመሢጥ ።
፲፬ ተክዐውኩ ፡ ከመ ፡ ማይ ፡ ወተዘርወ ፡ ኵሉ ፡ አዕፅምትየ
ወኮነ ፡ ልብየ ፡ ከመ ፡ ሠምዕ ፡ ዘይትመሠው ፡
በማዕከለ ፡ ከርሥየ ።
፲፭ ወየብሰ ፡ ከመ ፡ ገልዕ ፡ ኃይልየ ።
ወጠግዐ ፡ ልሳንየ ፡ በጕርዔየ ።
ወአውረድከኒ ፡ ውስተ ፡ መሬተ ፡ ሞት ።
፲፮ ዐገቱኒ ፡ ከለባት ፡ ብዙኃን ።
ወአኀዙኒ ፡ ማኅበሮሙ ፡ ለእኩያን ።
ቀነዉኒ ፡ እደውየ ፡ ወእገርየ ።
፲፯ ወኆለቁ ፡ ኵሎ ፡ አዕፅምትየ ።
እሙንቱሰ ፡ ጠየቁሙ ፡ ወተዐወሩኒ ።
፲፰ ወተካፈሉ ፡ አልባስየ ፡ ለርእሶሙ ።
ወተዓፀዉ ፡ ዲበ ፡ ዐራዝየ ።
፲፱ አንተ ፡ እግዚኦ ፡ ኢትርኃቅ ፡ እምኔየ ።
ወነጽር ፡ ውስተ ፡ ረዲኦትየ ።
፳ አድኅና ፡ እምኲናት ፡ ለነፍስየ ።
ወእምእደ ፡ ከለባት ፡ ለብሕቱትየ ።
፳፩ አድኅነኒ ፡ እምአፈ ፡ አንበሳ ።
ወእምአቅርንት ፡ ዘአሐዱ ፡ ቀርን ፡ ለብሕቱትየ ።
፳፪ እነግሮሙ ፡ ስመከ ፡ ለአኃውየ ።
ወበማእከለ ፡ ማኅበር ፡ እሴብሐከ ።
፳፫ እለ ፡ ትፈርህዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሰብሕዎ ።
ኵልክሙ ፡ ዘርዐ ፡ ያዕቆብ ፡ አክብርዎ ።
ወፍርህዎ ፡ ኵልክሙ ፡ ዘርዐ ፡ እስራኤል ።
፳፬ እስመ ፡ ኢመነነ ፡ ወኢተቆጥዐ ፡ ስእለተ ፡ ነዳይ ።
ወኢሜጠ ፡ ገጾ ፡ እምኔየ ።
ሶበ ፡ ጸራኅኩ ፡ ኀቤሁ ፡ ይሰምዐኒ ።
፳፭ እምኀቤከ ፡ ክብርየ ፡ በማኅበር ፡ ዐቢይ ።
ወእሁብ ፡ ብፅዐትየ ፡ በቅድመ ፡ እለ ፡ ይፈርህዎ ።
፳፮ ይብልዑ ፡ ነዳያን ፡ ወይጽገቡ ።
ወይሰብሕዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
ኵሎሙ ፡ እለ ፡ የኀሥሥዎ ።
ወየሐዩ ፡ ልቦሙ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ።
፳፯ ይዘከሩ፡ ወይትመየጡ፡ ኀበ፡ እግዚአብሔር ፡ ኵሎሙ
አጽናፈ ፡ ምድር ።
ወይስግዱ ፡ ቅድሜሁ፡ኵሎሙ፡በሐውርተ፡ አሕዛብ ።



በእስራኤል፡የተመሰገንህ፡አንተ፡ግን፡ በቅድስና፡ትኖራለህ ፫
አባቶቻችን፡አንተን፡ተማመኑ ፤ ፬
በመተማመናቸውም ፡ አዳንሃቸው ።
ወደ ፡ አንተ ፡ ጮኹ ፡ አመለጡም ፡ ፭
አንተንም ፡ ተማመኑ ፡ አላፈሩም ።
እኔ ፡ ግን ፡ ትል ፡ ነኝ ፡ ሰውም ፡ አይደለሁም ፤ ፮
የሰው ፡ ማላገጫ ፡ በሕዝብም ፡ ዘንድ ፡ የተናቅሁ ፡ ነኝ ።
የሚያዩኝ ፡ ሁሉ ፡ ይዘብቱብኛል ፤ ፯
ራሳቸውን ፡ እየነቀነቁ ፡ በከንፈሮቻቸው ፡
እንዲህ ፡ ይላሉ ፤
በእግዚአብሔር ፡ ተማመነ ፡ እስኪ ፡ ያድነውና ፡ ፰
የመውደዱን ፡ ልክ ፡ እንወቀው ፡ እያሉ ፡ ይታበያሉ ።
አንተ ፡ ግን ፡ ከእናቴ ፡ ማኅፀን ፡ አውጥተኸኛልና ፱
የእናቴን ፡ ጡት ፡ በምጠባበት ፡ ጊዜ፡ በአንተ ፡ ታመንሁ
ከማኅፀን ፡ ጀምሮ ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ ተጣልሁ ፡ ፲
ከእናቴ ፡ ማኅፀን ፡ ጀምረህ ፡ አንተ ፡ አምላኬ፡ነህ ።
ጭንቀት ፡ ቀርባለች ፡ ፲፩
ስለዚህ ፡ የሚረዳኝ ፡ የለምና ፡ ከእኔ ፡ አትራቅ ።
ብዙ ፡ በሬዎች ፡ ከበቡኝ ፡ ፲፪
የሰቡትና ፡ የደለቡ ፡ ፍሪዳዎችም ፡ ዞሩኝ ።
እንደ ፡ ነጣቂና ፡ እንደሚጮኽ ፡ አንበሳ ፡ ፲፫
በኔ ፡ ላይ ፡ አፋቸውን ፡ ከፈቱ ።
እንደ ፡ ውኃ ፡ ፈሰስሁ ፡ ፲፬
አጥንቶቼም ፡ ሁሉ ፡ ተለያዩ ፤
ልቤ ፡ እንደ ፡ ሰም ፡ ሆነ ፡
በአንጀቴም ፡ መካከል ፡ ቀለጠ ።
ኃይሌ ፡ እንደ ፡ ገል ፡ ደቀቀ ፡ ፲፭
መላሴም ፡ ከጉረሮዬና ፡ ከትናጌ ፡ ተጣጋ ፡
ወደ ፡ ሞትም ፡ አዘቅት ፡ አወረድኸኝ ።
ብዙ ፡ ውሾች ፡ ከበውኛልና ፤ ፲፮
በክፉ-ተኞች ፡ ጉባኤም ፡ ለፍርድ ፡ አቀረቡኝ ፡
እጆቼንና ፡ እግሮቼን ፡ ቸነከሩኝ ።
አጥንቶቼም ፡ ሁሉ ፡ ተቆጠሩ ፤ ፲፯
እነርሱም ፡ አዩኝ ፡ ተመለከቱኝም ።
ልብሶቼን ፡ ለያንዳንዳቸው ፡ ተከፋፈሉ ፡ ፲፰
በቀሚሴም ፡ ላይ ፡ ዕጣ ፡ ተጣጣሉ ።
አንተ ፡ ግን ፡ አቤቱ ፡ ከእኔ ፡ አትራቅ ፤ ፲፱
አንተ ፡ እኔን ፡ ለመርዳት ፡ ፍጠን ።
ነፍሴን ፡ ከሰይፍ ፡ ብቸኝነቴንም ፡ ከውሾች ፤ ፳
እጅ ፡ አድናት ።
ከአንበሳ ፡ አፍ ፡ አድነኝ ፡ ፳፩
ብቻነቴንም ፡ ልዩ፡ቀንድ ፡ ካላቸው ፡ አድን ።
ስምህን ፡ ለወንድሞቼ ፡ እነግራቸዋለሁ ፡ ፳፪
በአደባባይም ፡ መካከል ፡ አመሰግንሃለሁ ።
እግዚአብሔርን ፡ የምትፈሩ ፡ አመስግኑት ፡ ፳፫
የያዕቆብ ፡ ዘር ፡ ሁላችሁ ፡ አክብሩት ፡
የእስራኤልም ፡ ዘር ፡ ሁላችሁ ፡ ፍሩት ።
የችግረኛን ፡ ችግር ፡ አልናቀምና ፡ ቸልም ፡ አላለምና ፳፬
ፊቱንም ፡ ከእኔ ፡ አልሰወረምና ፡
ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እርሱ፡በጮኽሁ ፡ ጊዜ፡ሰማኝ ፡ እንጂ
በታላቅ፡ጉባኤ፡መካከል፤መከበሬያየ፡ከአንተ፡ዘንድ፡ነው ፳፭
እርሱን ፡ በሚፈሩት ፡ ፊት ፡ ስእለቴን ፡ እሰጣለሁ ።
የተራቡ ፡ ይበላሉ ፡ ይጠግቡማል ፤ ፳፮
እግዚአብሔርንም፡ የሚሹት ፡ ያመሰግኑታል ፤ ፳፯
ልባቸውም ፡ ለዘላለም ፡ ሕያው ፡ ይሆናል ።
የምድር ፡ ዳርቻዎች ፡ ሁሉ ፡ ያስቡ ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይመለሱ ፤
የአሕዛብ ፡ ነገዶች ፡ ሁሉ ፡ በፊቱ ፡ ይሰግዳሉ ።

፳፰ እስመ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ።
ወውእቱ ፡ ይኴንኖሙ ፡ ለአሕዛብ ።
፳፱ ብልዑ ፡ ወሰግዱ ፡ ኵሎሙ ፡ ጥሉላነ ፡ ምድር ።
ቅድሜሁ፡ይወድቁ፡ኵሎሙ፡እለ፡ይወርዱ፡ውስተ፡ምድር
፴ ነፍስየኒ ፡ ሎቱ ፡ ተሐዩ።ወዘርዕየኒ ፡ ሎቱ፡ ይትቀነይ ።
ትዜንዎ ፡ለእግዚአብሔር፡ትውልድ፡እንተ፡ ትመጽእ።
፴፩ ወይዜንዉ ፡ ጽድቀ ፡ ዚአሁ ።
ሕዝብ ፡ ዘይትወለድ ፡ ዘገብረ እግዚአብሔር ።

## መዝሙር ፡ ፳፪ ።

በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ እግዚአብሔር ፡ይሬእየኒ ፡ ወአልቦ ፡ ዘየኀጥአኒ ።
፪ ውስተ ፡ ብሔር ፡ ሥዑር ፡ ሀየ ፡ ያኀድረኒ ፡
ወኀበ ፡ ማየ ፡ ዕረፍት ፡ ሐፀነኒ ።
፫ ሜጠ ፡ ለነፍስየ ፡ ወመርሐኒ ፡ ፍኖተ ፡ ጽድቅ ።
በእንተ ፡ ስመ ፡ ዚአሁ ።
፬ እመኒ ፡ ሖርኩ ፡ ማእከለ ፡ ጽላሎተ ፡ ሞት ።
ኢይፈርህ ፡ ለእኩይ ፡ እስመ ፡ አንተ ፡ ምስሌየ ።
በትርከ ፡ ወቀስታምከ ፡ እማንቱ ፡ ገሠፃኒ ።
ወሠራዕከ ፡ ማእደ ፡ በቅድሜየ ።
፭ በአንጻሪሆሙ ፡ ለእለ ፡ ይሣቅዩኒ ።
ወአጽሐድከ ፡ በቅብዕ ፡ ርእስየ ።
ጽዋዕከኒ ፡ ጽኑዕ ፡ ወያረዊ ።
፮ ምሕረትከ ፡ ይትልወኒ ፡ በኵሉ ፡ መዋዕለ ፡ ሕይወትየ።
ከመ ፡ ታንብረኒ ፡ ቤተ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ለነዋህ ፡ መዋዕል ።

## መዝሙር ፡ ፳፫ ።

በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ ለእግዚአብሔር ፡ ምድር ፡ በምልኣ ።
ዓለምኒ ፡ ወኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይነብሩ ፡ ውስቴታ ።
፪ ወውእቱ ፡ በባሕር ፡ ሣረራ ።
ወበአፍላግኒ ፡ ውእቱ ፡ አጽንዓ ።
፫ መኑ ፡ የዐርግ ፡ ውስተ ፡ ደብረ ፡ እግዚአብሔር ።
ወመኑ ፡ ይቀውም ፡ ውስተ ፡ መካነ ፡ መቅደሱ ።
፬ ዘንጹሕ ፡ ልቡ ፡ ወንጹሕ ፡ እደዊሁ ።
ወዘኢነሥአ ፡ ከንቶ ፡ በላዕለ ፡ ነፍሱ ።
ወዘኢመሐለ ፡ በጒሕሉት ፡ ለቢጹ ።
፭ ውእቱ ፡ ይነሥእ ፡ በረከተ ፡ እምኀበ ፡ እግዚአብሔር ።
ወሣህሉኒ ፡ እምኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላኩ ።
፮ ዛቲ ፡ ትውልድ ፡ ተኀሦ ፡ ሎቱ ።
ወተኀሥሥ ፡ ገጾ ፡ ለአምላከ ፡ ያዕቆብ ።
፯ አርኅዉ ፡ ኆኃተ ፡ መኳንንት ።
ወይትረኃዋ ፡ ኆኃት ፡ እለ ፡ እምፍጥረት ።
ወይባእ ፡ ንጉሠ ፡ ስብሐት ።
፰ መኑ ፡ ውእቱ ፡ ዝንቱ ፡ ንጉ ፡ ስብሐት ።
እግዚአብሔር ፡ ኃያል ፡ ወጽኑዕ ።
እግዚአብሔር ፡ ኃያል ፡ በውስተ ፡ ጸብእ ።
፱ አርኅዉ ፡ ኆኃተ ፡ መኳንንት ።
ወይትረኃዋ ፡ ኆኃት ፡ እለ ፡ እምፍጥረት ።
ወይባእ ፡ ንጉሠ ፡ ስብሐት ።
፲ መኑ ፡ ውእቱ ፡ ዝንቱ ፡ ንጉሠ ፡ ስብሐት ።
እግዚአብሔር ፡ አምላከ ፡ ኃያላን ፡ ውእቱ ፡ ዝንቱ ፡
ንጉሠ ፡ ስብሐት ።



መንግሥት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ነውና ፡ ፳፰
እርሱም ፡ አሕዛብን ፡ ይገዛል ።
የምድር ፡ ተጠቃሚዎች፡ ሁሉ ፡ ይበላሉ ፡ ይሰግዳሉም ፳፱
ወደ ፡ መሬት፡የሚወርዱት ፡ ሁሉ፡በፊቱ ፡ ይንበረከካሉ
ነፍሴም ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ በሕይወት ፡ ትኖራለች ።
ዘሬ ፡ ይገዛለታል ። ፴
የምትመጣው፡ትውልድ ለእግዚአብሔር ፡ ትነግረዋለች
ለሚወለደውም ፡ ሕዝብ ፡እ ግ ዚ አ ብ ሔ ር ፡ ያደረ ፴፩
ገውን ፡ ጽድቁን ፡ ይነግራሉ ።

## መዝሙር ፡ ፳፪ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

እግዚአብሔር ፡ እረኛዬ ፡ ነው ፡ የሚያሳጣኝም ፡ የለም ፡ ፩

በለመለመ ፡ መስክ ፡ ያሰማራኛል ፡
ወደዕረፍት ፡ የመስኖ ፡ ውሃም ፡ ይመራኛል ። ፪
ነፍሴን ፡ መለሳት ፡ ፫
ስለ ፡ ስሙም ፡ በጽድቅ ፡ መንገድ ፡ መራኝ ።
በሞት ፡ ጥላ ፡ መካከል ፡ እንኳ ፡ ብሄድ ፤ ፬
አንተ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ነህና ፡ ክፉን ፡ አልፈራም ፡
በትርህና ፡ ምርኵዝህ ፡ እነርሱ ፡ ያጽናኑኛልና ።
በፊቱ ፡ ማዕድን ፡ አዘጋጀህልኝ ፡ ፭
በጠላቶቼ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ራሴን ፡ በዘይት ፡ ቀባህ ።
ጽዋዬም ፡ የተትረፈረፈ ፡ ነው ፤ ፮
ቸርነትህና ፡ ምሕረትህ ፡ በሕይወቴ ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡
ይከተሉኛል ፡
በእግዚአብሔርም፡ ቤት ፡ ለዘላለም ፡ እኖራለሁ ።

## መዝሙር ፡ ፳፫ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

ምድር ፡ በመላዋ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ናት ፤ ፩
ዓለምም ፡ በእርስዋም ፡ የሚኖሩ ፡ ሁሉ የሱ ፡ ናቸው
እርሱ ፡ በባሕሮች ፡ ላይ መሥርቶ ፡ ፪
በፈሳሾች ፡ አጽንቷታልና ።
ወደ ፡ እግዚአብሔር ተራራ ፡ ማን ፡ ይወጣል ? ፫
በቅድስናው ስፍራ ፡ ማን ፡ ይቆማል ?
እጆቹ ፡ የነጹ ፡ ልቡም ፡ ንጹሕ ፡ የሆነ ፡ ፬
ሰውነቱን ፡ ለከንቱ ፡ ነገር ፡ ያላነሣሣ ፡
ለባልንጀራውም ፡ በሐሰት ፡ ያልማለ ።
እርሱ ፡ በእግዚአብሔር ዘንድ ፡ በረከትን ፡ ፭
ከፈጣሪውም ፡ ምሕረትን ፡ ይቀበላል ።
ይህች ፡ ትውልድ ፡ እርሱን ፡ የምትፈልግ ፡ ፮
የያዕቆብን ፡ አምላክ ፡ ፊት፡ የምትሻ፡ ናት ።
እናንተ ፡ መኳንንቶች ፡ በሮችን ፡ ክፈቱ ፡ ፯
የዘላለም ፡ ደጆችም ፡ ይከፈቱ ፡
የክብርም ፡ ንጉሥ ፡ ይግባ ።
ይህ ፡ የክብር ፡ ንጉሥ ፡ ማን ፡ ነው ? ፰
እርሱ ፡ ብርቱና ፡ ኃያል ፡ የሚሆን ፡ እግዚአ
ብሔር ነው ።
እሱ ፡ በሰልፍ ፡ የበረታ ፡ኃያል ፡ እ ግ ዚ
አ ብ ሔ ር ፡ ነው ።
እናንተ ፡ መኳንንቶች ፡ በሮችን ፡ ክፈቱ ፡ ፱
የዘላለም ፡ ደጆችም ፡ ይከፈቱ ፡
የክብርም ፡ ንጉሥ ፡ ይግባ ።
ይህ ፡ የክብር ፡ ንጉሥ ፡ ማን ፡ ነው ? ፲
የኃያላን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡
እርሱ ፡ የክብር ፡ ንጉሥ ፡ ነው ።

መዝሙር ፡ ፳፬ ።

በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ ኀቤከ ፡ እግዚኦ ፡ አንቃዕዱኩ ፡ ነፍስየ ፡ አምላኪየ ።
፪ ወኪያከ ፡ ተወከልኩ ፡ እግዚኦ፡ ወኢይትኄፈር፡ ለዓለም
ወኢይሥሐቁኒ ፡ ጸላእትየ ።
፫ እስመ ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይሴፈዉከ ፡ ኢይትኄፈሩ ።
ለይትኄፈሩ ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይኤብሱ ፡ ዘልፈ ።
፬ ፍኖተከ ፡ እግዚኦ ፡ አምረኒ ።
ወአሠረ ፡ ዚአከ ፡ ምሀረኒ ።
ወምርሐኒ ፡ በጽድቅከ ።
፭ ወምሀረኒ ፡ እስመ ፡ አንተ ፡ አምላኪየ ፡ ወመድኀኒየ ።
ወኪያከ ፡ እሴፎ ፡ ኵሎ ፡ አሚረ ።
፮ ተዘከር ፡ ሣህለከ ፡ እግዚኦ ።
ወምሕረትከኒ ፡ እስመ ፡ ለዓለም ፡ ውእቱ ።
፯ ኃጢአትየ ፡ ዘበንእስየ ፡ ወእበድየ ፡ ኢትዝክር ፡ ሊተ ።
ወበከመ ፡ ሣህልከ ፡ ተዘከረኒ ።
በእንተ ፡ ምሕረትከ ፡ እግዚኦ ።
፰ ኄርኒ ፡ ወጻድቅኒ ፡ እግዚአብሔር ።
በእንተዝ ፡ ይመርሖሙ ፡ ፍኖተ ፡ ለእለ ፡ ይስሕቱ ።
፱ ወይሜህሮሙ ፡ ፍትሐ ፡ ለየዋሃን ።
ወይኤምሮሙ ፡ ፍኖተ ፡ ለልቡባን ።
፲ ኵሉ ፡ ፍኖ ቱ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሣህል ፡ ወጽድቅ ።
ለእለ ፡ የኃሡ ፡ ሕጎ ፡ ወስምዖ ።
በእንተ ፡ ስምከ ፡ እግዚኦ ።
፲፩ ወሥረይ ፡ ሊተ ፡ ኵሎ ፡ ኃጢአትየ ።
እስመ ፡ ብዙኅ ፡ ውእቱ ።
፲፪ መኑ ፡ ውእቱ ፡ ብእሲ ፡ ዘይፈርሆ ፡ ለእግዚአብሔር ።
ወይመርሖ ፡ ፍኖተ ፡ እንተ ፡ ኀርየ ።
፲፫ ወነፍሱሂ ፡ ውስተ ፡ ሠናይ ፡ ትኀድር ።
ወዘርዑሂ ፡ ይወርስዋ ፡ ለምድር ።
፲፬ ኃይሎሙ ፡ ውእቱ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለእለ ፡ ይፈርህዎ።
ወስሞሂ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ለእለ ፡ ይጼውዕዎ ።
ወሕጎሂ ፡ ይሜህሮሙ ፡
አዕይንትየሰ ፡ ዘልፈ ፡ ኀበ ፡ እግዚአብሔር ።
፲፭ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ይባልሆን ፡ እመሥገርት ፡ ለእገርየ ።
ነጽር ፡ ላዕሌየ ፡ ወተሣሀለኒ ።
፲፮ እስመ ፡ ባሕታዊ ፡ ወነዳይ ፡ አነ ።
፲፯ ወብዙኅ ፡ ኀዘኑ ፡ ለልብየ ።
አድኅነኒ ፡ እምንዳቤየ ።
፲፰ ርኢ ፡ ሕማምየ ፡ ወሥራሕየ ።
ወኅድግ ፡ ሊተ ፡ ኵሎ ፡ ኀጢአትየ ።
፲፱ ወርኢ ፡ ከመ ፡ በዝኁ ፡ ጸላእትየ ።
ጽልአ ፡ በዐመፃ ፡ ይጸልኡኒ ።
፳ ዕቀባ ፡ ለነፍስየ ፡ ወአድኅና ።
ወኢይትኀፈር ፡ እስመ ፡ ኪያከ ፡ ተወከልኩ ።
የዋሃን ፡ ወራትዓን ፡ ተለዉኒ ።
፳፩ እስመ ፡ ተሰፈውኩከ ፡ እግዚኦ ።
፳፪ ያድኅኖ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለእስራኤል ፡ እምኵሉ ፡
ምንዳቤሁ ።

መዝሙር ፡ ፳፭ ።

በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ ፍታሕ ፡ ሊተ ፡ እግዚኦ ፡ እስመ ፡ አንሰ ፡ በየዋሀትየ ፡
አሐውር ።
ወተወከልኩ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ከመ፡ ኢይድክም ።
፪ ፍትንኒ ፡ እግዚኦ ፡ ወአመክረኒ ።
ፍትን ፡ ልብየ ፡ ወኵልያትየ ።



መዝሙር ፡ ፳፬ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

አቤቱ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ነፍሴን ፡ አነሣለሁ ። ፩
አምላኬ ፡ አንተን ፡ ታምኜለሁና ፡ አልፈር ፤ ፪
ጠላቶቼም ፡ በእኔ ፡ አይሣቁብኝ ።
አንተን ፡ ተስፋ ፡ የሚያደርጉ ፡ አያፍሩም ፤ ፫
በከንቱ ፡ የሚገበዙ ፡ ግን ፡ ያፍራሉ ።
አቤቱ ፡ መንገድህን ፡ አመልክተኝ ፡ ፬
ፍለጋህንም ፡ አሳውቀኝ ።
አንተ ፡ የመድኃኒቴ ፡ አምላክ ፡ ነህና ፡ ፭
በጽድቅህ ፡ ምራኝ ፡ አስተምረኝም ፤
በዘመኑ ፡ ሁሉ ፡ አንተን ፡ ተስፋ ፡ አድርጌአለሁና ፡
አቤቱ ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ የነበሩትን ፡ ፮
ምሕረትህንና ፡ ቸርነትህን ፡ አስብ ።
የልጅነቴን ፡ ኃጢአትና ፡ መተላለፍ ፡ አታስብብኝ ፤ ፯
አቤቱ ፡ ስለ ፡ ቸርነትህ ፡ ብዛት ፡
እንደ ፡ ምሕረትህ ፡ አስበኝ ።
እግዚአብሔር ፡ ቸር ፡ ቅንም ፡ ነው ፤ ፰
ስለዚህ ፡ ኃጢአተኞችን ፡ በመንገድ ፡ ይመራቸዋል ።
ለደኃንች ፡ ጥበብን ፡ ይገልጻል ፡ ፱
ለቅኖችም ፡ ፍርድን ፡ ያስተምራቸዋል ።
ቃል ፡ ኪዳኑንና ፡ ትእዛዙን ፡ ለሚጠብቁ ፡ የእ ግ ዚ ፲
አ ብ ሔ ር ፡ መንገድ ፡ ሁሉ ፡ ቸርነትና ፡ እውነት ፡ ነው
አቤቱ ፡ ኃጢአቴ ፡ እጅግ ፡ የበዛ ፡ ነውና ፡ ፲፩
ስለ ፡ ስምህ ፡ ይቅር ፡ በለኝ ።
እግዚአብሔርን ፡ የሚፈራ ፡ ሰው ፡ ማን ፡ ነው ?
በሚመርጠው ፡ መንገድ ፡ ይመራው ፡ ዘንድ ።
ነፍሱ ፡ በመልካም ፡ ታድራለች ፡ ፲፪
ዘሩም ፡ ምድርን ፡ ይወርሳል ።
እግዚአብሔር፡ ለሚፈሩት ፡ ኃይላቸው ፡ ነው ፡
ቃል ፡ ኪዳኑንም ፡ ያስታውቃቸዋል ።
እርሱ ፡ እግሮቼን ፡ ከወጥመድ ፡ ያወጣቸዋልና ፡ ፲፫
ዓይኖቼ ፡ ሁል፡ጊዜ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር፡ ናቸው ።
እኔ ፡ ብቻዬን ፡ ችግረኛ ፡ ነኝና ፡ ፲፬
ፊትህን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አድርግ ፡ ማረኝም ።
የልቤ ፡ ችግር ፡ ብዙ ፡ ነው ፤ ፲፭
ከጭንቀቴ ፡ አውጣኝ ።
ድካሜንና ፡ መከራዬን ፡ ተመልከት ፡ ፲፮
ኃጢአቴንም ፡ ሁሉ ፡ ይቅር ፡ በለኝ ።
ጠላቶቼ ፡ እንደ ፡ በዙ ፡ አስተውል ፡ ፲፯
የግፍም ፡ ጥላቻ ፡ ጠልተውኛል ።
ነፍሴን ፡ ጠብቅና ፡ አድነኝ ፡ ፲፰
አንተን ፡ ታምኜለሁና ፡ አልፈር ።
አንተን ፡ ተስፋ ፡ አድርጌአለሁና ፡ ፲፱
የዋሃትና ፡ ቅንነት ፡ ይጠብቁኝ ።
አቤቱ ፡ እስራኤልን ፡ ከመከራው ፡ ሁሉ ፡ አድነው ። ፳

መዝሙር ፡ ፳፭ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

አቤቱ ፡ እኔ ፡ በየዋሃቴ ፡ ሄጃለሁና ፡ ፍረድልኝ ፤ ፩
በእግዚአብሔርም ፡ ታምኜለሁና ፡ አልናወጥም ።
አቤቱ ፡ ፍተነኝ ፡ መርምረኝም ፤ ፪
ኵላሊቴንና ፡ ልቤን ፡ ፍተን ።

፫ ከመ ፡ ምሕረትከ ፡ ቅድመ ፡ አዕይንትየ ፡ ውእቱ ።
ወተፈሣሕኩ ፡ በአድኅኖትከ ።
፬ ወኢነበርኩ ፡ ውስተ ፡ ዐውደ ፡ ከንቱ ።
ወኢቦእኩ ፡ ምስለ ፡ ዐማፅያን ።
፭ ጸላእኩ ፡ ማኅበረ ፡ እኩያን ።
ወኢይነብር ፡ ምስለ ፡ ጽልሕዋን ።
፮ ወአሐፅብ ፡ በንጹሕ ፡ እደውየ ።
ወአዐውድ ፡ ምሥዋዒከ ፡ እግዚኦ ።
ከመ ፡ እስማዕ ፡ ቃለ ፡ ስብሐቲከ ።
፯ ወከመ ፡ እንግር ፡ ኵሎ ፡ መንከረከ ።
፰ እግዚኦ ፡ አፍቀርኩ ፡ ሥነ ፡ ቤትከ ።
ወመካነ ፡ ማኅደረ ፡ ስብሐቲከ ።
፱ ኢትግድፋ ፡ ምስለ ፡ ኃጥአን ፡ ለነፍስየ ።
ወኢምስለ ፡ ዕደወ ፡ ደም ፡ ለሕይወትየ ።
፲ እለ ፡ ዐመፃ ፡ ውስተ ፡ እደዊሆሙ ።
ወምልዕት ፡ ህልያን ፡ የማኖሙ ።
፲፩ ወአንሰ ፡ በየዋሀትየ ፡ አሐውር ።
አድኅነኒ ፡ እግዚኦ ፡ ወተሣሀለኒ ።
፲፪ እስመ ፡ በርቱዕ ፡ ቆማ ፡ እገርየ ።
በማኅበር ፡ እባርከከ ፡ እግዚኦ ።



ምሕረትህ ፡ በዓይኔ ፡ ፊት ፡ ነውና ፡ ፫
በእውነትህም ፡ ተመላለስሁ ።
በከንቱ ፡ ሸንጎ ፡ አልተቀመጥሁም ፡ ፬
ከዓመፀኞችም ፡ ጋር ፡ አልተባበርኩም ።
የክፉዎችን ፡ ማኅበር ፡ ጠላሁ ፡ ፭
ከዝንጉዎችም ፡ ጋር ፡ አልቀመጥም ።
የምስጋናን ፡ ድምፅ ፡ እሰማ ፡ ዘንድ ፡ ፮
እጆቼን ፡ ንጹሕ ፡ አደርጋለሁ ።
ተአምራትህንም ፡ ሁሉ ፡ እነግር ፡ ዘንድ ፡ ፯
አቤቱ ፡ መሠዊያህን ፡ እዞራለሁ ።
አቤቱ ፡ የቤትህን ፡ ስፍራ ፡ ፰
የክብርህንም ፡ የማደሪያ ፡ ቦታ ፡ ወደድሁ ።
ከኃጢአተኞች ፡ ጋር ፡ ነፍሴን ፡ ፱
ከደም ፡ ሰዎችም ፡ ጋር ፡ ሕይወቴን ፡ አታጥፋ ፡
በእጃቸው ፡ ተንኰል ፡ አለባቸው ፡ ፲
ቀኛቸውም ፡ መማለጃ ፡ ተሞልታለች ።
እኔ ፡ ግን ፡ በየዋሃቴ ፡ ሄጃለሁ ፤ ፲፩
አድነኝ ፡ ማረኝም ።
እግሮቼ ፡ በቅንነት ፡ ቆመዋልና ፤ ፲፪
አቤቱ ፡ በማኅበር ፡ አመሰግንሃለሁ ።

መዝሙር ፡ ፳፮ ።

በእንተ ፡ ሕዝቅያስ ፡ አመ ፡ ደዌሁ ።

፩ እግዚአብሔር ፡ ያበርህ ፡ ሊተ ፡ ወያድኅነኒ ፡ ምንትኑ፡ ያፈርሀኒ ።
እግዚአብሔር ፡ ምእመና ፡ ለሕይወትየ ፡ ምንትኑ፡ ያደነግፀኒ ።
፪ ሶበ ፡ ይቀርቡኒ ፡ እኩያን ፡ ይብልዑኒ ፡ ሥጋየ ።
ጸላእትየሰ ፡ እለ ፡ ይሣቅዩኒ ፡ እሙንቱ ፡ ደከሙ ፡ ወወድቁ ።
፫ እመኒ ፡ ጸብዓኒ ፡ ተዐይን ፡ ኢይፈርሃኒ ፡ ልብየ ።
ወእመኒ ፡ ሮዱኒ ፡ ጸባዒት ፡ አንሰ ፡ ቦቱ ፡ ተወከልኩ ።
፬ አሐተ ፡ ሰአልክዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ወኪያሃ ፡ አኀሥሥ ፡
ከመ ፡ እኅድር ፡ ቤቶ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በኵሉ ፡ መዋዕለ ፡ ሕይወትየ
ወከመ ፡ ያርእየኒ ፡ ዘያሠምሮ ፡ ለእግዚአብሔር ።
ወከመ ፡ እፀመድ ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ መቅደሱ ።
፭ እስመ ፡ ኀብአኒ ፡ ውስተ፡ ጽላሎቱ ፡ በዕለተ፡ ምንዳቤየ
ወሠወረኒ ፡ በምኅባአ ፡ ጽላሎቱ ።
ወዲበ ፡ ኰኵሕ ፡ አልዐለኒ ።
፮ ናሁ ፡ ይእዜ ፡ አልዐለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ርእስየ ፡ ዲበ ፡ ጸላእትየ ።
ዖድኩ ፡ ወሦዕኩ ፡ ውስተ ፡ ደብተራሁ ።
መሥዋዕተ ፡ ወየበብኩ ፡ ሎቱ ።
እሴብሕ ፡ ወእዜምር ፡ ለእግዚአብሔር ።
፯ ስምዐኒ ፡ እግዚኦ ፡ ቃልየ ፡ ዘሰአልኩ ፡ ኀቤከ ።
ተሣሀለኒ ፡ ወስምዐኒ ፡ ለከ ፡ ይብለከ ፡ ልብየ ።
፰ ወኀሠሥኩ ፡ ገጸከ ። ገጸ ፡ ዚአከ ፡ አኀሥሥ ፡ እግዚኦ ።
፱ ወኢትሚጥ ፡ ገጸከ ፡ እምኔየ ።
ወኢትትገሐሥ ፡ እምገብርከ ፡ ተምዒዐከ ።
ረዳኤ ፡ ኩነኒ ፡ ወኢትግድፈኒ ።
ወኢትትኀየየኒ ፡ አምላኪየ ፡ ወመድኅኒየ ።
፲ እስመ ፡ አቡየ ፡ ወእምየ ፡ ገደፉኒ ።
ወእግዚአብሔር ፡ ተወከፈኒ ።
፲፩ ምርሐኒ ፡ እግዚኦ ፡ ፍኖተከ ።
ወምርሐኒ ፡ ፍኖተ ፡ ርትዕከ ፡ በእንተ ፡ ጸላእትየ ።
ወኢትመጥወኒ ፡ ለነፍሰ ፡ እለ ፡ ይሣቅዩኒ ።

መዝሙር ፡ ፳፮ ።

ስለ ፡ ሕዝቅያስ ።

እግዚአብሔር ፡ ብርሃኔና ፡ መድኃኒቴ ፡ ነውና ፤ ፩
የሚያስፈራኝ ፡ ምንድን ፡ ነው ?
እግዚአብሔር ፡ የሕይወቴ ፡ መታመኛዋ ፡ ነውና ፡
የሚያስደነግጠኝ ፡ ምንድር ፡ ነው ።
ክፉዎች ፡ አስጨናቂዎች ፡ ጠላቶቼም ፡ ፪
ሥጋዬን ፡ ይበሉ ፡ ዘንድ ፡ በቀረቡ ፡ ጊዜ ፡
እነርሱ ፡ ተሰናክለው ፡ ወደቁ ።
ጠላትም ፡ ቢከበኝ ፡ ልቤ ፡ አይፈራም ፤ ፫
ሰልፍም ፡ ቢነሣብኝ ፡ በዚህ ፡ እተማመናለሁ ።
እግዚአብሔርን ፡ አንዲት ፡ ነገር ፡ ለመንሁት ፡ ፬
እርስዋንም ፡ እሻለሁ ፤ በሕይወቴ ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ እኖር ፡ ዘንድ ፤
እግዚአብሔርን ፡ ደስ ፡ የሚያሰኘውንም ፡ አይ ፡ ዘንድ
መቅደሱንም ፡ እመለከት ፡ ዘንድ ፡ ነው ።
በመከራዬ ፡ ቀን ፡ በድንኳኑ ፡ ሰውሮኛልና ፡ ፭
በድንኳኑም ፡ መሸሸጊያ ፡ ሸሽጎኛልና ፡
በአደባባይም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አድርጎኛልና ።
እነሆ ፡ አሁን ፡ በዙሪያ ፡ ባሉ ፡ በጠላቶቼ ፡ ላይ ፡ ፮
ራሴን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረገ ፤
በድንኳኑም ፡ የምስጋና ፡ መሥዋዕትን ፡ ሠዋሁ ፤
ለእግዚአብሔር ፡ እቀኛለሁ ፡ እዘምርለትማለሁ ።
አቤቱ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ የጮኩትን ፡ ቃሌን ፡ ስማኝ ፤ ፯
ማረኝ ፡ አድምጠኝም ።
አንተ ፡ ፊቴን ፡ እሹት ፡ብለኸልና ፡ አቤቱ ፡ ፊትህን ፰
እሻለሁ ፡ ልቤም ፡ አንተን ፡ አንተን ፡ አለ ።
ፊትህን ፡ ከእኔ ፡ አታዞር ፡ ፱
ተቆጥተህ ፡ ከባሪያህ ፡ ፈቀቅ ፡ አትበል ፤
ረዳት ፡ ሁነኝ ፡ አትጣለኝም ፡
የመድኃኒቴም ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ አትተወኝ ።
አባቴና ፡ እናቴ ፡ ጥለውኝ ፡ ነበርና ፡ ፲
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ተቀበለኝ ።
አቤቱ ፡ መንገድህን ፡ አስተምረኝ ፡ ፲፩
ስለ ፡ ጠላቶቼም ፡ በቀና ፡ መንገድ ፡ ምራኝ ።

፲፪ እስመ ፡ ቆሙ ፡ ላዕሌየ ፡ ሰማዕተ ፡ ዐመፃ ።
ወሐሰት ፡ ርእሰ ፡ ዐመፃ ።
፲፫ እትአመን ፡ ከመ ፡ እርአይ ፡ ሠናየ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
በብሔረ ፡ ሕያዋን ።
፲፬ ወተሰፈዎ ፡ ለእግዚአብሔር ።
ተዐገሥ፡ወአጽንዕ፡ልበከ ። ወተሰፈዎ፡ ለእግዚአብሔር

መዝሙር ፡ ፳፯ ።

በእንተ ፡ ሕዝቅያስ ።

፩ ኀቤከ ፡ እግዚኦ ፡ ጸራኅኩ ፡ አምላኪየ ፡ ወኢትጸመመኒ
ወኢመሰል ፡ ተጸመምከኒ ፡ እከውን ፡ ከመ ፡ እለ ፡ ይወርዱ
ውስተ ፡ ግብ ።
ስምዐኒ ፡ እግዚኦ ፡ ቃለ ፡ ስእለትየ ፡ ዘጸራኅኩ ፡ ኀቤከ።
፪ ሶበ ፡ እነሥእ ፡ እደውየ ፡ በጽርሐ ፡ መቅደስከ ።
፫ ኢትስሐበ ፡ ምስለ ፡ ኃጥኣን ፡ ለነፍስየ ።
ወኢትግድፈኒ ፡ ምስለ ፡ ገበርተ ፡ ዐመፃ ።
እለ ፡ ይትናገሩ ፡ ሰላመ ፡ ምስለ ፡ ቢጾሙ ።
ወእኩይ ፡ ውስተ ፡ ልቦሙ ።
፬ ሀቦሙ ፡ በከመ ፡ ምግባሮሙ ።
ወበከመ ፡ እከየ ፡ ሕሊናሆሙ ።
ፍድዮሙ ፡ በከመ ፡ ግብረ ፡ እደዊሆሙ ።
ፍድዮሙ ፡ ፍዳሆሙ ፡ ላዕለ ፡ ርእሶሙ ።
፭ እስመ ፡ ኢሐለዩ ፡ ውስተ ፡ ግብረ ፡ እግዚአብሔር ።
ወኢውስተ ፡ ግብረ ፡ እደዊሁ ።
ንሥቶሙ ፡ ወኢትሕንጾሙ ።
፮ ይትባረክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እስመ ፡ ሰምዐኒ ፡
ቃለ ፡ ስእለትየ ።
፯ እግዚአብሔር ፡ ረዳኢየ ፡ ወምእመንየ ፡
ወቦቱ ፡ ተወከለ ፡ ልብየ ፡ ወይረድአኒ ።
፰ ወሠረፀ ፡ ሥጋየ ፡ ዘእምፈቃድየ ፡ እአምኖ ።
እግዚአብሔር ፡ ኀይሎሙ ፡ ውእቱ ፡ ለሕዝቡ ።
ወምእመነ ፡ መድኀኒተ ፡ መሲሑ ፡ ውእቱ ።
፱ አድኅን ፡ ሕዝበከ ፡ ወባርክ ፡ ርስተከ ።
ረዐዮሙ ፡ ወአልዕሎሙ ፡ እስከ ፡ ለዓለም ።

መዝሙር ፡ ፳፰ ።

በእንተ ፡ ሕዝቅያስ፡ አመ ፡ ሐይወ ፡ እምደዌሁ ።

፩ አምጽኡ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ውሉደ ፡ አማልክት ።
አምጽኡ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ዕጐለ ፡ ሐራጊት ።
አምጽኡ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ክብረ ፡ ወስብሐተ ።
፪ አምጽኡ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስብሐተ ፡ ለስሙ ።
ስግዱ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በዐፀደ ፡ መቅደሱ ።
፫ ቃለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ላዕለ ፡ ማያት ።
አምላከ ፡ ስብሐት ፡ አንጐድጐደ ።
እግዚአብሔር ፡ ላዕለ ፡ ማያት ፡ ብዙኀ ።
፬ ቃለ ፡ እግዚአብሔር ፡ በኀይል ።
ቃለ ፡ እግዚአብሔር ፡ በዐቢይ ፡ ስብሐት ።
፭ ቃለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይቀጠቅጥ ፡ አርዘ ።
ወይቀጠቅጦ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለአርዘ ፡ ሊባኖስ ።
፮ ወያደገድጎ ፡ ከመ ፡ ላሕመ ፡ ሊባኖስ ።
ወፍቁርሰ ፡ ከመ ፡ ወልደ ፡ ዘአሐዱ ፡ ቀርኑ ።
፯ ቃለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይመትር ፡ ነደ ፡ እሳት ።
፰ ቃለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያድለቀልቆ ፡ ለገዳም ።
ወያድለቀልቆ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሐቅለ ፡ ቃዴስ ፡
፱ ቃለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያጸንዖሙ ፡ ለሀየላት ።
ወይከሥት ፡ አዕዋመ ።
ወበጽርሑሰ ፡ ኵሉ ፡ ይብል ፡ ስብሐት ።



የሐሰት፡ምስክሮችና፡ዓመፀኞች፡ተነሥተውብኛልና ፡ ፲፪
ለጠላቶቼ ፡ ፈቃድ ፡ አሳልፈህ ፡ አትስጠኝ ።
የእግዚአብሔርን ቸርነት ፡ በሕያዋን፡ ምድር፡ አይ፡ ዘንድ፡ አምናለሁ ። ፲፫
እግዚአብሔርን ፡ተስፋ ፡ አድርግ ፤ ፲፬
በርታ ፡ ልብህም ፡ ይጽና ፤
እግዚአብሔርን ፡ተስፋ ፡ አድርግ ።

መዝሙር ፡ ፳፯ ።

ስ ለ ሕ ዝ ቅ ያ ስ ።

አቤቱ ፡ ወደ፡አንተ፡ እጠራለሁ ፤ ዝም ፡ ብትለኝ ፡ ፩
ወደ ፡ ጕድጓድ ፡ እንደሚወርዱት ፡ እንዳልመስል ፡
አንተ ፡ አምላኬ ፡ ዝም ፡ አትበለኝ ።
ወደ ፡ መቅደስህ ፡ ማደሪያ ፡ እጄን ፡ ባነሣሁ ፡ ጊዜ ፡ ፪
ወደ ፡ አንተ ፡ የጮኽሁትን ፡ የልመናዬን ፡ ቃል ፡ ስማ ።
ከኃጥአንና፡ከክፉ፡አድራጊዎች፡ጋር፡ነፍሴን፡አትውሰዳት፤ ፫
ክፋትም ፡ በልባቸው ፡ እያለ ፡ ከባልንጀሮቻቸው ፡ ጋር ፡
ሰላም ፡ ከሚናገሩት ፡ ጋር ፡ አትጣለኝ ።
እንደ፡ሥራቸው፡እንደ፡አካሄዳቸውም፡ ክፋት፡ስጣቸው፤ ፬
እንደ ፡ እጃቸውም ፡ ሥራ ፡ ክፈላቸው ፡
ፍዳቸውን ፡ ወደ ፡ ራሳቸው ፡ መልስ ።
ወደ እግዚአብሔር ፡ ሥራ ፡ ወደ ፡ እጆቹም ፡ ፭
ተግባር ፡ አላስተዋሉምና ፡ ያፈርሳቸዋል ፡ አንጂ ፡
አይሠራቸውም ።
የልመናዬን ፡ ቃል ፡ ሰምቶኛልና ፡ ፮
እግዚአብሔር ፡ ይመስገን ።
እግዚአብሔር ፡ ኃይሌና ፡ ጋሻዬ ፡ ነው ፤ ፯
እሱ ፡ ረዳቴ ፡ ነው፡ልቤ ፡ በእርሱ ፡ ይተማመናል ፤
ሥጋዬም ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፡
በሙሉ ፡ ፈቃዴኝነትም ፡ አመሰግነዋለሁ ።
እግዚአብሔር ፡ ለሕዝቡ ፡ ኃይላቸው ፡ ነው፤ ፰
ለቀባውም ፡ የመድኃኒቱ ፡ መታመኛ ፡ ነው ።
ሕዝብህን ፡ አድን ፡ ርስትህንም ፡ ባርክ ፤ ፱
ጠብቃቸው ፡ ለዘላለሙም ፡ ከፍ፡ ከፍ ፡ አድርጋቸው ።

መዝሙር ፡ ፳፰ ።

ስለሕዝቅያስ ፡ ከደዌው ፡ በዳነ ፡ ጊዜ ።

እ ና ን ተ ፡ የአምላክ ፡ ልጆች ፡ ለእግዚአብ ፩
ሔር፡ ክብርን ፡ ስጡ ።
ምስጋናንም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አቅርቡ ።
የስሙን ፡ ልዕልና ፡ለእግዚአብሔር፡ አምጡ ፡ ፪
በቅድስናው ፡ ስፍራ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ስገዱ ።
የእግዚአብሔር ፡ ድምፅ ፡ በውኆች ፡ ላይ ፡ ይሰፋል ፤ ፫
የክብር ፡ አምላክ ፡ አንጐደጐደ ፤
እግዚአብሔር ፡ በባሕሮች ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ነው ።
የእግዚአብሔር ፡ ድምፅ ፡ በኃይል ፡ ነው ፡ ፬
የእግዚአብሔር ፡ ድምፅ ፡ በታላቅ ፡ ክብር፡ ነው ።
የእግዚአብሔር ፡ ድምፅ ፡ ዝግባን ፡ ይሰብራል ፡ ፭
እግዚአብሔር ፡ የሊባኖስን ፡ ዝግባ ፡ ይቆርጣል ።
ሊባኖስን ፡ እንደ ፡ ጥጃ ፡ ስርዮንንም ፡ እንደ ፡ አው ፮
ራሪስ ፡ ልጅ ፡ ያዘልላቸዋል ።
የእግዚአብሔር ፡ ድምፅ የእሳቱን ፡ ነበልባል ፡ ይከፋፍለዋል ። ፯

የእግዚአብሔር ፡ ድምፅ ምድረ ፡ በዳውን ፡ ያናውጣል ፡ ፰
እግዚአብሔር ፡ የቃዴስን ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ያንቀጠቅጣል ።
የእግዚአብሔር ፡ ድምፅ፡ዋሊያዎችን፡ያጠነክራቸዋል ፤ ፱
ጫካዎቹንም ፡ ይመነጥራቸዋል ፤
ሁሉም ፡ በየበኩሉ ፡ ምስጋና ፡ ያቀርባል ።

፲ እግዚአብሔር ፡ ያስተጋብእ ፡ ለማየ ፡ አይኅ ።
ይነብር ፡ እግዚአብሔር ፡ ወይነግሥ ፡ ለዓለም ።
፲፩ ወይሁቦሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ ኀይለ ፡ ለሕዝቡ ።
እግዚአብሔር ፡ ይባርኮሙ ፡ ለሕዝቡ ፡ በሰላም ።

መዝሙር ፡ ፳፱ ።

በእንተ ፡ ሕዝቅያስ ።

፩ አአኵተከ ፡ እግዚኦ ፡ እስመ ፡ ተወከፍከኒ ።
ወሰላተ ፡ ጸላኢ ፡ ኢረሰይከኒ ።
፪ እግዚኦ ፡ አምላኪየ ፡ ጸራኅኩ ፡ ኀቤከ ፡ ወተሣሀልከኒ።
፫ እግዚኦ ፡ አውፃእካ ፡ እምሲኦል ፡ ለነፍስየ ።
ወአድኀንከኒ ፡ እምእለ ፡ ይወርዱ ፡ ውስተ ፡ ግብ ።
፬ ዘምሩ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ጻድቃኑ ።
ወግነዩ ፡ ለዝክረ ፡ ቅድሳቲሁ ።
፭ እስመ ፡ መቅሠፍት ፡ እመዓቱ፡ ወሕይወት፡ እምፈቃዱ ።
በምሴት ፡ ይደምጽ ፡ ብካይ ፡ ወበጽባሕ ፡ ፍሥሓ ።
፮ አንሰ ፡ እቤ ፡ በተድላየ ፡ ኢይትሀወክ ፡ ለዓለም ።
፯ እግዚኦ ፡ በሥምረትከ ፡ ሀባ ኀይለ ፡ ለሕይወትየ ።
ሜጥከሰ ፡ ገጸከ ፡ ወኮንኩ ፡ ድንጉፀ ።
፰ ኀቤከ ፡ እግዚኦ ፡ ጸራኅኩ ፡ ኀበ ፡ አምላኪየ ፡
ወእስእል ።
፱ ምንተ ፡ ያሰልጥ ፡ ደምየ ፡ ለእመ ፡ ወረድኩ ፡ ውስተ ፡
ሙስና ።
መራትኑ ፡ የአምነከ ፡ ወይነግር ፡ ጽድቀከ ።

፲ ሰምዐ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወተሣሀለኒ ።
ወኮነኒ ፡ እግዚአብሔር ፡ ረዳኢየ ።
ሜጥከ ፡ ላሕየ ፡ ወአስተፍሣሕከኒ ።
ሠጠጥከ ፡ ሠቅየ ፡ ወሐሜት ፡ አቅነትከኒ ።
፲፩ ከመ ፡ እዘምር ፡ ለከ ፡ ክብርየ ፡ ወኢይደንግፅ ።
፲፪ እግዚኦ ፡ አምላኪየ ፡ እገኒ ፡ ለከ ፡ ለዓለም ።

መዝሙር ፡ ፴ ።

በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ ኪያከ ፡ ተወከልኩ ፡ እግዚኦ ፡ ወኢይትኀፈር ፡ ለዓለም
ወበጽድቅከ ፡ አንግፈኒ ፡ ወባልሀኒ ።
፪ አጽምዕ ፡ እዝነከ ፡ ኀቤየ ፡ ወፍጡነ ፡ አድኅነኒ ።
ኩነኒ ፡ አምላኪየ ፡ ወመድኀኒየ ።
ወቤተ ፡ ፀወንየ ፡ ከመ ፡ ታድኅነኒ ።
፫ እስመ ፡ ኀይልየ ፡ ወፀወንየ ፡ አንተ ።
በእንተ ፡ ስምከ ፡ ምርሐኒ ፡ ወሴስየኒ ።
ወአውፅአኒ ፡ እምዛቲ፡መሥገርት፡እንተ፡ኀብኡ፡ሊተ ።
፬ እስመ ፡ አንተ ፡ ረዳኢየ ፡ እግዚኦ ።
፭ ውስተ ፡ እዴከ ፡ አመኀፅን ፡ ነፍስየ ።
ቤዝወኒ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላከ ፡ ጽድቅ ።
፮ ጸላእከ ፡ እግዚኦ ፡ ኵሎ ፡ ዘየዐቅብ ፡ ከንቶ ፡ ለዝሉፉ ።
ወአንሰ ፡ በእግዚአብሔር ፤ ተወከልኩ ።
እትፌሣሕ ፡ ወእትሐሠይ ፡ በአድኅኖትከ ።
፯ እስመ ፡ ርኢከኒ ፡ በሕማምየ ።
ወአድኀንካ ፡ እምንዳቤሃ ፡ ለነፍስየ ።
፰ ወኢዘጋሕከኒ ፡ ውስተ ፡ እደ ፡ ፀርየ ።
ወአቀምኮን ፡ ውስተ ፡ መርሕብ ፡ ለእገርየ ።



እግዚአብሔር ፡ የጥፋት ፡ ውኃን ፡ ያከማቻል ፡ ፲
እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ ንጉሥ ፡ ይኖራል ።
እግዚአብሔር ፡ ለሕዝቡ ፡ ኃይልን ፡ ይሰጣል ፡ ፲፩
እግዚአብሔር ፡ ሕዝቡን ፡ በሰላም ፡ ይባርካል ።

መዝሙር ፡ ፳፱ ።

ስለ ሕዝቅያስ ።

አቤቱ ፡ ተቀብለኸኛልና ፡ ጠላቶቼንም ፡ ደስ ፡ ፩
አላሰኘሀብኝምና ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደርግሃለሁ ።
አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ጮኽሁ ። ፪
ምሕረትም ፡ አደረግህልኝ ፡
አቤቱ ፡ ነፍሴን ፡ ከሲኦል ፡ አወጣሃት ፡ ፫
ወደ ፡ ጕድጓድም ፡ እንዳልወርድ ፡ አዳንኸኝ ።
ቅዱሳን ፡ ሆይ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ዘምሩ ፡ ፬
ለቅድስናውም ፡ መታሰቢያ ፡ አመስግኑ ።
ቍጣው ፡ ለጥቂት ፡ ጊዜ ፡ ነው ፡ ፭
ሞገሱ ፡ ግን ፡ ለብዙ ፡ የሕይወት ፡ ዘመን ፡ ነውና ፡
ማታ ፡ ልቅሶ ፡ ይሰማል ፡
ጠዋት ፡ ግን ፡ ደስታ ፡ ይሆናል ።
እኔም ፡ በደስታዬ ፡ ለዘላለም ፡ አልታወክም ፡ አልሁ ። ፮
አቤቱ ፡ በፈቃድህ ፡ ለሕይወቴ ፡ ኃይልን ፡ ሰጠሃት ፤ ፯
ፊትህን ፡ መለስህ ፡ እኔም ፡ ደነገጥሁ ።
አቤቱ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ጠራሁ ፡ ፰
ወደ ፡ አምላኬም ፡ ለመንሁ ።
ወደ ፡ ጥፋት ፡ ብወርድ ፡ በደሜ ፡ ምን ፡ ጥቅም ፡ አለ ? ፱
አፈር ፡ ያመሰግንሃልን ? ጽድቅህንም ፡ ይናገራልን ?

እግዚአብሔር ፡ ሰማ ፡ ማረኝም ፤
እግዚአብሔር ፡ ረዳቴ ፡ ሆነኝ ።
ክብሬ ፡ ትዘምርልህ ፡ ዘንድ ፡ ዝምም ፡ እንዳትል ፡ ፲፩
ልቅሶዬን ፡ ለደስታ ፡ ለወጥህልኝ ፤
ማቄን ፡ ቀደህ ፡ ደስታን ፡ አስታጠቅኸኝ ።
አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ ለዘላለሙ ፡ አመሰግንሃለሁ ። ፲፪

መዝሙር ፡ ፴ ።

ስለ ትሩፋን ።

አቤቱ ፡ አንተን ፡ ታምኛለሁና ፡ ለዘላለም ፡ አልፈር ፤ ፩
በጽድቅህም ፡ አድነኝ ።
ጆሮህን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አዘንብል ፡ ፈጥነህም፡ አድነኝ ፤ ፪
ታድነኝ ፡ ዘንድ ፡ የመታመኛ ፡ አምላክና ፡
የመጠጊያ ፡ ቤት ፡ ሁነኝ ።
አምባዬና ፡ መጠጊያዬ ፡ አንተ ፡ ነህና ፡ ፫
ስለ ፡ ስምህ ፡ መንገዱን ፡ አቅና ፡ ምራኝም ።
አንተ ፡ መታመኛዬ ፡ ነህና ፡ ፬
ከሸመቁብኝ ፡ ወጥመድ ፡ አውጣኝ ።
በእጅህ ፡ ነፍሴን ፡ እሰጣለሁ ፤ ፭
የእውነት ፡ አምላክ ፡ አቤቱ ፡ ታድገኸኛልና ።
ከንቱ ፡ ምናምንቴነትን ፡ የጠበቁትን ፡ ጠላህ ፤ ፮
እኔ ፡ ግን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ታመንሁ ።
መከራዬን ፡ አይተሃልና ፡ ፯
ነፍሴንም ፡ ከጭንቀት ፡ አድነሃታልና ፡
በምሕረትህ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፡ ሐሤትም ፡ አደርጋለሁ ።
በጠላቴ ፡ እጅ ፡ አልዘጋህብኝም ፤ ፰
በሰፊም ፡ ስፍራ ፡ እግሮቼን ፡ አቆምክ ።

፱ ተማሀለኒ ፡ እግዚኦ ፡ እስመ ፡ ሐመምኩ ።
ወተሀውከት ፡ እመዓት ፡ ዐይንየ ።
ነፍስየኒ ፡ ወከርሥየኒ ።
፲ እስመ ፡ ኀልቀ ፡ በሕማም ፡ ሕይወትየ ።
ወዓመትየኒ ፡ በገዓር ።
ወደክመ ፡ በተጽናስ ፡ ኃይልየ ።
ወአንቀልቀለ ፡ ኵሉ ፡ አዕፅምትየ ።
፲፩ ወተጽእልኩ ፡ በኀበ ፡ ኵሎሙ ፡ ጸላእትየ ።
ወፈድፋደሰ ፡ በኀበ ፡ ጎርየ ።
ግሩም ፡ ኮንክዎሙ ፡ ለአዝማድየ ።
እለኒ ፡ ይሬእዩኒ ፡ አፍአ ፡ ይጕዩ ፡ እምኔየ ።
፲፪ ቀብጹኒ ፡ እምልብ ፡ ከመ ፡ ዘሞተ ።
ወኮንኩ ፡ አመ ፡ ንዋይ ፡ ዘተሀጕለ ።
፲፫ እስመ ፡ ሰማዕኩ ፡ ደምፀ ፡ ብዙኃን ፡ እለ ፡ ዐገቱኒ ፡
ዐውድየ ።
ሶበ ፡ ተጋብኡ ፡ ኅቡረ ፡ ላዕሌየ ።
ወተማከሩ ፡ ይምስጥዋ ፡ ለነፍስየ ።
፲፬ ወአንሰ ፡ ብከ ፡ ተወከልኩ ፡ እግዚኦ ።
ወእቤለከ ፡ አምላኪየ ፡ አንተ ።
፲፭ ውስተ ፡ እዴከ ፡ ርስትየ ።
አድኅነኒ ፡ እምእደ ፡ ፀርየ ፡ ወእምእለ ፡ ሮዱኒ ።
፲፮ አብርህ ፡ ገጸከ ፡ ላዕለ ፡ ገብርከ ።
ወአድኅነኒ ፡ በእንተ ፡ ምሕረትከ ።
፲፯ ወኢይትኀፈር ፡ እግዚኦ ፡ እስመ ፡ ጸዋዕኩከ ።
ለይትኃፈሩ ፡ ጽልሕዋን ፡ ወይረዱ ፡ ውስተ ፡ ሲኦል።
፲፰ አሉ ፡ ለን ፡ ለከናፍረ ፡ ጕሕሉት ።
እለ ፡ ይነባ ፡ ዐመፃ ፡ ላዕለ ፡ ጻድቅ ።
በትዕቢት ፡ ወበመንኖ ።
ወበከመ ፡ ብዝኀ ፡ ምሕረትከ ፡ እግዚኦ ።
ሰወርኮሙ ፡ ለእለ ፡ ይፈርሁከ ።
፲፱ ወአድኅንኮሙ ፡ ለእለ ፡ ይትዌከሉ ፡ ብከ ።
በቅድመ ፡ ደቂቀ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ።
፳ ወተኀብእሙ ፡ በጽላሎትከ ፡ እምሀከከ ፡ ሰብእ ።
ወትከድኖሙ ፡ በመንጦላዕትከ ፡ እምባህለ ፡ ልሳን ።
፳፩ ይትባረክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዘሰብሐ ፡ ምሕረቶ ፡
ላዕሌየ ፡ በብዝኃ ፡ ምንዳቤየ ።
፳፪ አንሰ ፡ እቤ ፡ ተገደፍኩኑ ፡ እንጋ ፡ እምቅድመ ፡ አዕይንቲከ ።
በእንተዝ ፡ ሰምዐኒ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃለ ፡ ስእለትየ ፡
ዘጸራሕኩ ፡ ኀቤሁ ።
፳፫ አፍቅርዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ኵልክሙ ፡ ጻድቃኑ ።
እስመ ፡ ጽድቀ ፡ የኀሥሥ ፡ እግዚአብሔር ።
ወይትቤቀሎሙ፡ ለእለ፡ የኀሥሡ ፡ ትዕቢተ፡ ፈድፋደ።
ተዐገሡ ፡ ወአጽንዑ ፡ ልበክሙ ።
፳፬ ኵልክሙ ፡ እለ ፡ ተወከልክሙ ፡ በእግዚአብሔር ።



መዝሙር ፡ ፴፩ ።
በእንተ ፡ ሕዝቅያስ ።

፩ ብፁዓን ፡ እለ ፡ ተኀድገ ፡ ሎሙ ፡ ኃጢአቶሙ ።
ወእለ ፡ ኢሐሰበ ፡ ሎሙ ፡ ኵሎ ፡ ጌጋዮሙ ።
፪ ብፁዕ ፡ ብእሲ ፡ ዘኢኈለቈ ፡ ሎቱ ፡ እግዚአብሔር ፡ ኃጢአቶ ።
ወዘአልቦ ፡ ጽልሑት ፡ ውስተ ፡ ልቡ ።
እስመ ፡ አርመምኩ ፡ በሊየ ፡ አዕፅምትየ ።
እምኀበ ፡ እጸርሕ ፡ ኵሎ ፡ አሚረ ።
፫ እስመ ፡ መዓልተ፡ወሌሊተ ፡ ከብደት፡ እዴከ ፡ ላዕሌየ።
፬ ወተመየጥኩ ፡ ለኀርትምና ፡ ሶበ ፡ ወግዐኒ ፡ ሦክ ።



ተቸግሬአለሁና ፡ አቤቱ ፡ ምራኝ ፤ ፱
ዓይኔም ፡ ከኀዘን ፡ የተነሣ ፡ ሟሟች ፤
ሰውነቴም ፡ ሁሉ ፡ ታወከ ።
ሕይወቴ ፡ በኀዘን ፡ አልቃለችና ፤ ፲
ዓመታቴም ፡ በልቅሶ ፡ ጨኸት ፡ ተፈጸመ ፤
ኃይሌ ፡ ከችጋር ፡ የተነሣ ፡ ደከመ ፤
አጥንቶቼም ፡ ተቀጠቀጡ ።
በጠላቶቼ ፡ ዘንድ ፡ ተነወርሁ ፤ ፲፩
ይልቁንም ፡ በጎረቤቶቼ ፡ ዘንድ ፡ ተናቅሁ ፤
ለሚያውቁኝም ፡ ማስፈራሪያ ፡ ሆንሁ ፤
በሜዳ ፡ ያዩኝም ፡ ከእኔ ፡ ሸሹ ።
እንደ ፡ ሞተ ፡ ሰው ፡ ከልብ ፡ ተረሳሁ ፤ ፲፪
እንደ ፡ ተበላሸ ፡ ዕቃም ፡ ሆንሁ ።
የብዙ ፡ ሰዎችን ፡ ስድብ ፡ ሰምቻለሁና ፤ ፲፫
በአካባቢዬ ፡ ፍርሃት ፡ ሰፈነ ፤
በእኔ ፡ ላይ ፡ በአንድነት ፡ በተሰበሰቡ ፡ ጊዜ ፤
ነፍሴን ፡ ለመንጠቅ ፡ ተማከሩ ።
አቤቱ ፡ እኔ ፡ ግን ፡ በአንተ ፡ ታመንሁ ፤ ፲፬
አንተም ፡ አምላኬ ፡ ነህ ፡ አልሁ ።
ሕይወቴ ፡ በእጅህ ፡ ነውና ፤ ፲፭
ከጠላቶቼ ፡ እጅና ፡ ከሚያሳድዱኝ ፡ አድነኝ ።
የፊትህን ፡ ብርሃን ፡ በባሪያህ ፡ ላይ ፡ አብራ ፤ ፲፮
እንደ ፡ ቸርነትህም ፡ አድነኝ ።
አቤቱ ፡ አንተን ፡ ጠርቻለሁና ፡ አልፈር ፤ ፲፯
ክፉዎች ፡ ግን ፡ ይፈሩ ፤
ወደሲኦልም ፡ ይውረዱ ።
በድፍረትና ፡ በትዕቢት ፡ በመናቅም ፤ ፲፰
በጻድቅ ፡ ላይ ፡ ነቀፋን ፡ የሚሰነዝሩ ፤
የሽንገላ ፡ ከንፈሮች ፡ ድዳ ፡ ይሁኑ ።

በአንተ፡ ለሚያምኑ፡ በሰው፡ ልጆች፡ፊት ፡ ያዘጋጀሃት፡ ፲፱
ለሚፈሩህም ፡ የሰወርሃት፡ ቸርነትህ ፡ እንደምን ፡ በዛች ።
በፊትህ ፡ መጋረጃ ፡ ከሰው ፡ ክርክር ፡ ትጋርዳቸዋለህ ፤ ፳
በድንኳንህም ፡ ከአንደበት ፡ ክርክር ፡ ትሸፍናቸዋለህ ።
በተከበበ ፡ ከተማ ፡ የሚያስደንቅ ፡ ምሕረቱን ፡ በእኔ ፡ ፳፩
የገለጠ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይመስገን ።
እኔስ፡ ከዓይንህ፡ ፊት፡ተጣልሁ፡በድንጋጤም፡ተዋጥሁ፤ ፳፪
አንተ ፡ ግን ፡ ወደ፡ አንተ፡በጮኽሁ ፡ ጊዜ ፡
የልመናዬን ፡ ቃል ፡ ሰማኸኝ ።
ሁላችሁ ፡ ቅዱሳኑ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ውደዱት ፤ ፳፫
እግዚአብሔር ፡ እውነተኞችን ፡ ይፈልጋል ፤
ትዕቢተኞችንም ፡ ፈጽሞ ፡ ይበቀላቸዋል ።
እግዚአብሔርን ፡ የምታምኑ ፡ ሁላችሁ ፤ ፳፬
በርቱ ፡ ልባችሁም ፡ ይጽና ።



መዝሙር ፡ ፴፩ ።
ስለ ሕዝቅያስ ።

ሕግ ፡ መተላለፉ ፡ የቀረችለት ፤ ፩
ኃጢአቱም ፡ የተሠረየችለት ፡ ምስጉን ፡ ነው ።
እግዚአብሔር ፡ በደሉን ፡ የማይቆጥርበት ፡ ፪
በመንፈሱም፡ ሽንገላ፡ የሌለበት፡ ሰው ፡ ምስጉን፡ ነው ።
ሁል ፡ ጊዜ ፡ ከመጮኼ ፡ የተነሣ ፤ ፫
ዝም ፡ ባልሁ ፡ ጊዜ ፡ አጥንቶቼ ፡ ተበላሹ ፤
በቀንና ፡ በሌሊት ፡ እጅህ ፡ ከብዳብኛለችና ።
ቀዝቃዛውም ፡ ሰውነቴ ፡ ለጋለ ፡ ትኵሳት ፡ ተለወጠ ። ፬

፭ ኃጢአትየ ፡ ነገርኩ ፡ ወኢሰወርኩ ፡ ኢ.ኀባእኩ ።
ወእቤ ፡ እስተዋደ ፡ ርእስየ ፡ ኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡
በእንተ ፡ ኃጢአትየ ።
ወአንተ ፡ ኀደግ ፡ ጽልሑቶ ፡ ለልብየ ።
፮ በእንተዝ ፡ ይጼሊ ፡ ኀቤከ ፡ ኵሉ ፡ ጻድቅ ፡ በጊዜ ፡ ርቱዕ ።
ወባሕቱ ፡ ማየ ፡ አይኅ ፡ ብዙኅ ፡ ኢይቀርብ ፡ ኀቤከ ።
፯ አንተ ፡ ምስካይየ ፡ እምሥቃይ ፡ ምንዳቤየ ፡ እንተ ፡ ረከበተኒ ።
ወትፍሥሕትየኒ ፡ ከመ ፡ ታድኅነኒ ፡ እምእለ ፡ ሮዱኒ።
፰ አሌብወከ ፡ ወአጸንዐከ ፡ በዛቲ ፡ ፍኖት ፡ እንተ ፡ ሖርከ ።
ወአጸንዕ ፡ አዕይንትየ ፡ ላዕሌከ ።
ኢትኩኑ ፡ ከመ ፡ ፈረስ ፡ ወበቅል ፡ እለ ፡ አልቦሙ ፡ ልብ ።
እለ ፡ በሕማል ፡ ወበልጓም ፡ ይመይጥዎሙ ፡ መላትሒሆሙ
፱ ከመ ፡ ኢይቅረቡ ፡ ኀቤከ ።
፲ ብዙኅ ፡ መቅሠፍቶሙ ፡ ለኃጥኣን ፡
ወእለሰ ፡ ይትዌከሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ሣህል ፡ ይሜግቦሙ ።
፲፩ ተፈሥሑ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ወተሐሠዩ ፡ ጻድቃን ።
ወተመክሑ ፡ ኵልክሙ ፡ ርቱዓነ ፡ ልብ ።

መዝሙር ፡ ፴፪ ።

በእንተ ፡ ሕዝቅያስ ።

፩ ተፈሥሑ ፡ ጻድቃን ፡ በእግዚአብሔር ።
ወለራትዓን ፡ ይደልዎሙ ፡ ክብር ።
፪ ግነዩ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በመሰንቆ ።
ወበመዝሙር ፡ ዘዐሠርቱ ፡ አውታሪሁ ፡ ዘምሩ ፡ ሎቱ ፡
፫ ወሰብሕዎ ፡ ስብሐተ ፡ ሐዲሰ ።
ሠናየ ፡ ዘምሩ ፡ ወየብቡ ፡ ሎቱ ።
፬ እስመ ፡ ጽድቅ ፡ ቃሉ ፡ ለእግዚአብሔር ።
ወኵሉ ፡ ግብሩ ፡ በሃይማኖት ።
፭ ያፈቅር ፡ እግዚአብሔር ፡ ጽድቀ ፡ ወምጽዋተ ።
ሣህሉ ፡ ለእግዚአሔር ፡ መልአ ፡ ምድረ ።
፮ ወበቃለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸንዓ ፡ ሰማያት ።
ወእምእስትንፋሰ ፡ አፉሁ ፡ ኵሉ ፡ ኀይሎሙ ።
፯ ዘያስተጋብእ ፡ ከመ ፡ ዝቅ ፡ ለማየ ፡ ባሕር ።
ወይሠይሞ ፡ ውስተ ፡ መዛግብት ፡ ቀላያት ።
፰ ትፈርሆ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ኵላ ፡ ምድር ።
ወእምኔሁ ፡ ይደነግፁ ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይነብሩ ፡ ውስተ ፡ ዓለም ።
፱ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ይቤ ፡ ወኮኑ ። ወውእቱ ፡ አዘዘ ፡ ወተፈጥሩ ።
፲ እግዚአብሔር ፡ ይመይጥ ፡ ምክሮሙ ፡ ለአሕዛብ ።
ወይመይጥ ፡ ሕሊናሆሙ ፡ ለሕዝብ ።
ወያረስዮሙ ፡ ምክሮሙ ፡ ለመላእክት ።
፲፩ ወምክሩሰ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ይሄሉ ፡ ለዓለም ።
ወሕሊና ፡ ልቡኒ ፡ ለትውልደ ፡ ትውልድ ።
፲፪ ብፁዕ ፡ ሕዝብ ፡ ዘእግዚአብሔር ፡ አምላኩ ።
ሕዝብ ፡ ዘኀረየ ፡ ሎቱ ፡ ለርስቱ ።
፲፫ እምሰማይ ፡ ሐወጸ ፡ እግዚአብሔር ።
ወርእየ ፡ ኵሎ ፡ ደቂቀ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ።
፲፬ ወእምድልው ፡ ጽርሑ ፡ መቅደሱ ።
ወርእየ ፡ ላዕለ ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ ኅዱራን ፡ ዲበ ፡ ምድር
፲፭ ዘውእቱ ፡ ባሕቲቱ ፡ ፈጠረ ፡ ልቦሙ ።
ወዘየአምር ፡ ኵሎ ፡ ምግባሮሙ ።
፲፮ ኢይድኅን ፡ ንጉሥ ፡ በብዝኀ ፡ ሠራዊቱ ።
ወያርብሕኒ ፡ ኢይድኅን ፡ በብዝኀ ፡ ኀይሉ ።

ኃጢአቴን ፡ ለአንተ ፡ አስታወቅሁ ፡ ፭
በደሌንም ፡ አልሸፈንሁም ፤
ለእግዚአብሔር፡ መተላለፌን ፡ እንግራለሁ ፡ አልሁ ፤
አንተም ፡ የልቤን ፡ ኃጢአት ፡ ይመሰስህልኝ ።
ስለዚህ ፡ ቅዱስ ፡ ሁሉ ፡ በምቹ ፡ ጊዜ ፡ ፮
ወደ ፡ አንተ ፡ ይለምናል ፤
ብዙ ፡ የጥፋት ፡ ውኃም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ አይቀርብም ።
አንተ ፡ ለእኔ ፡ መሸሸጊያዬ ፡ ነህ ፤ ፯
ከጭንቅም ፡ ታወጣኛለህ ።
ከከበቡኝ ፡ ታድነኝ ፡ ዘንድ ፡ መመኪያዬ ፡ ነህ ፤ ፰
አስተምርሃለሁ ፡ በምትሄድበትም ፡ መንገድ ፤
እመራሃለሁ ፤ ወደ ፡ አንተ ፡ እንዳይቀርቡ ፡
ዓይኖቼ ፡ አንተን ፡ ይመለከታሉ ።
በልባብና፡ በልጓም፡ ጉንጫቸውን፡እንደሚለጒሟቸው ፡ ፱
ማስተዋልም ፡ እንደሌላቸው ፡
እንደ ፡ ፈረስና ፡ እንደ ፡ በቅሎ ፡ አትሁኑ ።
በኃጢአተኛ ፡ ብዙ ፡ መቅሠፍት ፡ ይታዘዝበታል ። ፲
በእግዚአብሔር ፡ የሚታመነውን ፡ ግን ፡ ምሕረት ፡ ይቅርታ ፡
ይደረግለታል ።
ጻድቃን፡ ሆይ፡ ደስ፡ ይበላችሁ ፡ ሐሤትንም ፡ አድርጉ ፡ ፲፩
ልባችሁም ፡ የቀና ፡ ሁላችሁ ፡ እልል ፡ በሉ ።

መዝሙር ፡ ፴፪ ።

ስለ ሕዝቅያስ ።

ጻድቃን፡ሆይ፡በእግዚአብሔር፡ደስ ፡ ይበላችሁ ።
ለቅኖች ፡ ምስጋና ፡ ይገባል ።
እግዚአብሔርን ፡ በመሰንቆ ፡ አመስግኑት ፡
ዓሥር ፡ አውታርም ፡ ባለው ፡ በገና ፡ ዘምሩለት ።
አዲስ ፡ ቅኔንም ፡ ተቀኙለት ፡ ፫
በእልልታም ፡ መልካም ፡ ዝማሬን ፡ ዘምሩ ።
የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ዕውነት ፡ እንደሆነ ፡
ሥራውም ፡ ሁሉ ፡ የታመነ ፡ ነውና ።
ጽድቅንና ፡ ዕውነተኛ ፡ ፍርድን ፡ ይወዳል ፤ ፭
የእግዚአብሔር ፡ ቸርነት ፡ ምድርን ፡ መላች ።
በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ሰማዮች ፡ ጸኑ ፡
ሠራዊታቸውም ፡ ሁሉ ፡ በአፉ ፡ እስትንፋስ ፡ ተገኙ ።
የባሕርን ፡ ውኃ ፡ እንደ ፡ ረዋት ፡ ይሰበስበዋል ፤ ፯
ቀላዮችንም ፡ በመዝገቦች ፡ ያኖራቸዋል ።
ምድር ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ትፍራው ፡ ፰
በዓለም፡የሚኖሩ፡ሁሉም፡ከእርሱ ፡የተነሣ፡ ይደንግጡ ።
አንድ ፡ ጊዜ ፡ ተናግሮአልና ፡ ተከናወኑ ፤ ፱
እርሱም ፡ እንደአዘዘ ፡ ጸኑ ።
እግዚአብሔር ፡ የአሕዛብን ፡ ምክር ፡ ያጠፋል ፡ ፲
ሃሳባቸውንም ፡ ይበትናል ።
የእግዚአብሔር ፡ ምክር ፡ ግን ፡ ለዘላለም ፡ ይኖራል ፡ ፲፩
የልቡም ፡ አሳብ ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ይተላለፋል ።
እግዚአብሔር ፡ አምላኩ ፡ የሚሆንለት ፡ ፲፪
ሕዝብ ፡ ምስጉን ፡ ነው ፡
እርሱ ፡ ለርስቱ ፡ የመረጠው ፡ ሕዝብ ፡ ይሆናልና ።
እግዚአብሔር ፡ ከሰማይ ፡ ተመለከተ ፡ ፲፫
የሰውንም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ አየ ።
እርሱ ፡ ብቻውን ፡ ልባቸውን ፡ የሠራ ፡ ፲፬
ሥራቸውንም ፡ ሁሉ ፡ የሚያስተውል ።
ከማደሪያው ፡ በታ ፡ ሆኖ ፡ በምድር ፡ ፲፭
ወደሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡ ተመለከተ ።
ንጉሥ ፡ በሠራዊቱ ፡ ብዛት ፡ አይድንም ፡ ፲፮
ኃያልም ፡ በኃይሉ ፡ ብዛት ፡ አያመልጥም ።

፲፯ ወፈረስኒ ፡ ሐሰት ፡ ኢያድኅን ።
ወኢያመሥጥ ፡ በብዝኀ ፡ ጽንዑ ።
፲፰ ናሁ፡አዕይንቲሁ፡ ለእግዚአብሔር ኀበ፡እለ፡ይፈርህዎ።
ወእለሰ ፡ ይትዌከሉ ፡ በምሕረቱ ።
፲፱ ያድኅና ፡ እሞት ፡ ለነፍሶሙ ።
ወይሴስዮሙ ፡ እመ ፡ ረኃብ ።
፳ ነፍስነሰ ፡ ትሴፈዎ ፡ ለእግዚአብሔር ።
እስመ ፡ ረዳኢነ ፡ ወምስካይነ ፡ ውእቱ ።
፳፩ እስመ ፡ ቦቱ ፡ ይትፌሣሕ ፡ ልብነ ።
ወተወከልነ ፡ በስሙ ፡ ቅዱስ ።
፳፪ ለትኩን ፡ እግዚኦ ፡ ምሕረትከ ፡ ላዕሌነ ።
ወበከመ ፡ ላዕሌከ ፡ ተወከልነ ።

መዝሙር ፡ ፴፫ ።

በእንተ ፡ ሕዝቅያስ ።

፩ እባርኮ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ።
ወዘልፈ ፡ ስብሐቲሁ ፡ ውስተ፡ አፉየ ።
በእግዚአብሔር ፡ ትከብር ፡ ነፍስየ ።
ይስምዑ ፡ የዋሃን ፡ ወይትፌሥሑ ።
፫ አዕብይዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ምስሌየ ።
ወናልዕል ፡ ስሞ ፡ ኅቡረ ።
፬ ኀሠሥክዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ወተሰጥወኒ ።
ወእምኵሉ ፡ ምንዳቤየ ፡ አድኀነኒ ።
፭ ቅረቡ ፡ ኀቤሁ ፡ ወያበርህ ፡ ለክሙ ።
ወኢይትኃፈር ፡ ገጽክሙ ።
፮ ዝንቱ ፡ ነዳይ ፡ ጸርኀ ፡ ወእግዚአብሔር ፡ ሰምዖ ።
ወእምኵሉ ፡ ምንዳቤሁ ፡ አድኃኖ ።
፯ ይትዐየን ፡ መልአከ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዐውዶሙ ።
ለእለ ፡ ይፈርህዎ ፡ ወያድኅኖሙ ።
፰ ጠዐሙ ፡ ወታእምሩ ፡ ከመ ፡ ኄር ፡ እግዚአብሔር ።
ብፁዕ ፡ ብእሲ ፡ ዘተወከለ ፡ ቦቱ ።
ፍርህዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ኵልክሙ ፡ ቅዱሳኑ ።
፱ እስመ ፡ አልቦሙ ፡ ተጽናስ ፡ ለእለ ፡ ይፈርህዎ ።
፲ ብዑላንሰ ፡ ነድዩ ፡ ወርኀቡ ።
ወእለሰ፡የኀሥሥዎ፡ ለእግዚአብሔር ኢተጸነሱ፡እምኵሉ ፡ ሠናያት ።
፲፩ ንዑ ፡ ደቂቅየ ፡ ወስምዑኒ ።
ፈሪሀ ፡ እግዚአብሔር ፡ እምሀርክሙ ።
፲፪ መኑ ፡ ውእቱ ፡ ብእሲ ፡ ዘይፈቅድ ፡ ሐዩወ ።
ወያፈቅር ፡ ይርአይ ፡ መዋዕለ ፡ ሠናያተ ።
፲፫ ክላእ ፡ ልሳነከ ፡ እምእኩይ ።
ወከናፍሪከኒ ፡ ከመ ፡ ኢይንብባ ፡ ጕሕሉተ ።
፲፬ ተገሐሥ ፡ እምእኩይ ፡ ወግበር ፡ ሠናየ ።
ኅሥሥ ፡ ለሰላም ፡ ወዴግና ።
፲፭ እስመ ፡ አዕይንቲሁ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ኀበ ፡ ጻድቃኑ
ወእዝኑሂ ፡ ኀበ ፡ ስእለቶሙ ።
ገጹ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ኀበ ፡ እለ ፡ ይገብሩ ፡ እኩየ ።
፲፮ ከመ ፡ ይሠሩ ፡ ምድር ፡ ዝክሮሙ ።
፲፯ ጸርሑ ፡ ጻድቃን ፡ ወእግዚአብሔር ፡ ሰምዖሙ ።
ወእምኵሉ ፡ ምንዳቤሆሙ ፡ አድኃኖሙ ።
፲፰ ቅሩብ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለየዋሃነ ፡ ልብ ።
ወያድኅኖሙ ፡ ለትሑታነ ፡ መንፈስ ።
፲፱ ብዙኅ ፡ ሕማሞሙ ፡ ለጻድቃን ።
ወእምኵሉ ፡ ያድኅኖሙ ፡ እግዚአብሔር ።
፳ እግዚአብሔር ፡ የዐቅብ ፡ ኵሎ ፡ አዕዕምቲሆሙ ።
ወኢይትቀጠቀጥ ፡ አሐዱ ፡ እምውስቴቶሙ ።
፳፩ ሞቱ ፡ ለኃጥእ ፡ ጸዋግ ።
ወእለሰ ፡ ይጸልእዎ ፡ ለጽድቅ ፡ ይኔስሑ ።
፳፪ ይቤዙ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነፍሰ ፡ አግብርቲሁ ።
ወኢይኔስሑ ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይትዌከሉ ፡ ቦቱ ።



ፈረሱም ፡ ከንቱ ፡ ነው ፡ ኢያድንም ፤
በኃይሉም ፡ ብዛት ፡ ኢያመልጥም ። ፲፯
እነሆ ፡ የእግዚአብሔርዓይኖች፡ ወደሚፈሩት፡ ናቸው፡ ፲፰
በምሕረቱም ፡ ወደሚታመኑ ።
ነፍሳቸውን ፡ ከሞት ፡ ያድን ፡ ዘንድ ፡ ፲፱
በራብም ፡ ጊዜ ፡ ይመግባቸው ፡ ዘንድ ፡ ይመለከታል ።
ሰውነታችን ፡ እግዚአብሔርንትሰፋ፡ ታደርገዋለች ፡ ፳
ረዳታችንና ፡ መጠጊያችን ፡ እርሱ ፡ ነውና ።
ልባችን ፡ በእርሱ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፡ ፳፩
በቅዱስ ፡ ስሙ ፡ ታምነናልና ።
አቤቱ ፡ በአንተ ፡ እንደመታመናችን ፡ ፳፪
ምሕረትህ ፡ በላያችን ፡ ትሁን ።

መዝሙር ፡ ፴፫ ።

ስለሕዝቅያስ ።

እግዚአብሔርን ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ እባርከዋለሁ ፤ ፩
ምስጋናውንም ፡ ዘወትር ፡ በአፌ ፡ እናገራለሁ ።
ነፍሴ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ትከብራለች ፡ ፪
ደጋጎችም ፡ ሰምተው ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
እግዚአብሔርን ከእኔ ፡ ጋር ፡ ታላቅ ፡ አድርጉት ፡ ፫
በአንድነትም ፡ ስሙን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ እናድርግ ።
እግዚአብሔርን ፡ ፈለግሁት ፡ መለሰልኝም ፡ ፬
ከመከራዬም ፡ ሁሉ ፡ አዳነኝ ።
ወደ ፡ እርሱ ፡ ቅረቡ ፡ ያበራላችሁማል ፡ ፭
ፊታችሁም ፡ አይጨልምም ።
ይህ ፡ ችግረኛ ፡ ጮኸ ፡ እግዚአብሔርም፡ ሰማው ፡ ፮
ከመከራውም ፡ ሁሉ ፡ አዳነው ።
የእግዚአብሔር ፡ መልአክ ፡ በሚፈሩት ፡ ሰዎች ፡ ፯
ዙሪያ ፡ ይሰፍራል ፡ ያድናቸውማል ።
እግዚአብሔር ፡ ቸር ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ዕወቁ ፤ ፰
በእርሱ ፡ የሚታመን ፡ ሰው ፡ ምስጉን ፡ ነው ።
የሚፈሩት ፡ አንዳችን ፡ ኢያጡምና ፤ ፱
ቅዱሳኑ ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፍሩት ።
ባለጠጎች ፡ ደኸዩ ፡ ተራቡም ፡ ፲
እግዚአብሔርንየሚፈልጉት፡ግን፡ከመልካም፡ነገር፡ሁሉ፡ አይጐድልባቸውም
እግዚአብሔርን፡ መፍራት፡እስተምራችሁ፡ዘንድ፡ ፲፩
ልጆቼ ፡ ኑ ፡ ስሙኝ ።
ሕይወትን ፡ የሚፈቅድ ፡ ሰው ፡ ማን ፡ ነው ? ፲፪
በጎንም ፡ ዘመን ፡ ለማየት ፡ የሚወድ ?
አንደበትህን ፡ ከፉ ፡ ከመናገር ፡ ከልክል ፤ ፲፫
ከንፈሮችህም ፡ ሽንገላን ፡ አይናገሩ ።
ከክፉ ፡ ሽሽ ፡ መልካምንም ፡ አድርግ ፤ ፲፬
ሰላምን ፡ እሻ ፡ ተከተላትም ።
የእግዚአብሔር ፡ ዓይኖች ፡ ወደ ፡ ጻድቃን ፡ ፲፭
ጆሮቹም ፡ ወደ ፡ ጩኸታቸው ፡ ናቸውና ።
መታሰቢያቸውን ፡ ከምድር ፡ ያጠፋ ፡ ዘንድ ፤ ፲፮
የእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉን፡ በሚያደርጉ፡ላይ፡ ነው ።
ጻድቃን ፡ ጮኹ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ሰማቸው ፤ ፲፯
ከመከራቸውም ፡ ሁሉ ፡ አዳናቸው ።
እግዚአብሔር ፡ ልባቸው ፡ ለተሰበረ ፡ ቅርብ ፡ ነው ፤ ፲፰
መንፈሳቸው ፡ የተሰበረውንም ፡ ያድናቸዋል ።
የጻድቃን ፡ መከራቸው ፡ ብዙ ፡ ነው ፡ ፲፱
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ከሁሉ ፡ ያድናቸዋል ።
እግዚአብሔር ፡ አጥንቶቻቸውን ፡ ሁሉ ፡ ይጠብቃል ፡ ፳
ከእነርሱም ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፡ አይሰበርም ።
ኃጢአተኞችን ፡ ክፋታቸው ፡ ያጠፋቸዋል ፤ ፳፩
ጻድቃንንም ፡ የሚጠሉ ፡ ይጸጸታሉ ።
የባሪያዎቹን ፡ ነፍስ እግዚአብሔር ፡ ይታደጋል ፡ ፳፪
በእርሱም ፡ የሚያምኑ ፡ ሁሉ ፡ አይጸጸቱም ።

መዝሙር ፡ ፴፬ ።

በእንተ ፡ ኤርምያስ ።

፩ ግፍዖሙ ፡ እግዚኦ ፡ ለእለ ፡ ይገፍዑኒ ።
ጽብአሙ ፡ እግዚኦ ፡ ለእለ ፡ ይጸብኡኒ ።
፪ ንሣእ ፡ ወልታ ፡ ወኲናተ ፡ ወተንሥእ ፡ ውስተ ፡ ረዲኦትየ ።
፫ ምላሕ ፡ ሰይፈከ ፡ ወዕግቶሙ ፡ ለእለ ፡ ሮዱኒ ።
በሎ ፡ ለነፍስየ ፡ አነ ፡ ውእቱ ፡ ረዳኢኪ ።
፬ ለይትኀፈሩ ፡ ወይኅሰሩ ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ የኀሥሥዋ ፡ ለነፍስየ ።
ለይግብኡ ፡ ድኅሬሆሙ ፡ ወይትኀፈሩ ፡ እለ ፡ መከሩ ፡ እኩየ ፡ ላዕሌየ
፭ ለይኩኑ ፡ ከመ ፡ ጸበል ፡ ዘቅድመ ፡ ገጸ ፡ ነፋስ ።
ወመልአከ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለይሣቅዮሙ ።
፮ ለትኩን ፡ ፍኖቶሙ ፡ ዳኅፀ ፡ ወጽልመተ ።
ወመልአከ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለይስድዶሙ ።
፯ እስመ ፡ በከንቱ ፡ ኀብኡ ፡ሊተ ፡ መሥገርተ ፡ ያጥፍኡኒ ።
ወበከንቱ ፡ አመንዘዝዋ ፡ ለነፍስየ ።
፰ ለትምጽኦሙ ፡ መሥገርት ፡ እንተ ፡ ኢያእመሩ ።
ወተአኀዞሙ ፡ መሥገርት ፡ እንተ ፡ ኀብኡ ።
ወይደቁ ፡ ውስተ ፡ ይእቲ ፡ መሥገርት ።
፱ ነፍስነሰ ፡ ትትፌሣሕ በእግዚአብሔር ።
ወትትሐሠይ ፡ በአድኅኖቱ ።
፲ ኵሉ ፡ አዕፅምትየ ፡ ይብሉከ ። እግዚኦ ፡ መኑ ፡ ከማከ ።
ታድኅኖ ፡ ለነዳይ ፡ እምእደ ፡ ዘይትዔገሎ ።
ለነዳይ ፡ ወለምስኪን ፡ እምደ ፡ ዘይመሥጦ ።
፲፩ ተንሥኡ ፡ ላዕሌየ ፡ ሰማዕተ ፡ ዐመፃ ።
ወዘኢየአምር ፡ ነበቡ ፡ ላዕሌየ ።
፲፪ ፈደዩኒ ፡ እኪተ ፡ ህየንተ ፡ ሠናይት ።
ወእኅጥእዋ ፡ ውሉደ ፡ ለነፍስየ ።
፲፫ ወአንሰ ፡ ሶበ ፡ አስርሐኒ ፡ ለበስኩ ፡ ሰቀ ።
ወአሕመምክዋ ፡ በጾም ፡ ለነፍስየ ።
ወጸሎትየኒ ፡ ገብአ ፡ ውስተ ፡ ሕፅንየ ።
፲፬ ከመ ፡ ዘለእኁውየ ፡ ወለቢጽየ ፡ ከማሁ ፡ አድሎኩ ።
ከመ ፡ ዘይላሁ ፡ ወይቴክዝ ፡ ከማሁ ፡ አትሐትኩ ፡ ርእስየ ።
፲፭ ተጋብኡ ፡ ላዕሌየ ፡ ወተፈሥሑ ።
ተማከሩ ፡ ይቅሥፉኒ ፡ ወኢየአመርኩ ።
ተሰብሩሂ ፡ ወኢደንገፁ ።
፲፮ ፈተኑኒ ፡ ወተሣለቁ ፡ ላዕሌየ ፡ ወሰሐቁኒ ።
ወሐቀዩ ፡ ስነኒሆሙ ፡ ላዕሌየ ።
፲፯ እግዚኦ ፡ ማእዜኑ ፡ ትሬኢ ፡ ሊተ ።
አድኅና ፡ ለነፍስየ ፡ እምእከዮ ፡ ምግባሮሙ ።
ወእምአናብስት ፡ ለብሕቱትየ ።
፲፰ እገኒ ፡ ለከ ፡ እግዚኦ ፡ በውስተ ፡ ማኅበር ፡ ዐቢይ ።
ወእሴብሐከ ፡ በውስተ ፡ ሕዝብ ፡ ክቡድ ።
፲፱ ወኢይትፈሥሑ ፡ ላዕሌየ ፡ እለ ፡ ይጻልኡኒ ፡ በዐመፃ ።
እለ ፡ ይፃረሩኒ ፡ በከንቱ ፡ ወይትቃጸቡኒ ፡ በአዕይንቲሆሙ ።
፳ እስመ ፡ ሊተሰ ፡ ሰላመ ፡ ይትናገሩኒ ።
ወይመክሩ ፡ በቍጽር ፡ ያመንስዉኒ ።
፳፩ ወአብቀዉ ፡ አፉሆሙ ፡ ላዕሌየ ።
ወይቤሉ ፡ እንቋዕ ፡ እንቋዕ ፡ ርኢናሁ ፡ በአዕይንቲነ ።
፳፪ ርኢ ፡ እግዚኦ ፡ ወኢታርምም ።
እግዚኦ ፡ ኢትርኃቅ ፡ እምኔየ ።
፳፫ ተንሥእ ፡ እግዚኦ ፡ ወአጽምዕ ፡ ፍትሕየ ።
አምላኪየ ፡ ወእግዚእየ ፡ ውስተ ፡ ቅስትየ ።
፳፬ ፍታሕ ፡ ሊተ ፡ እግዚኦ ፡ አምላኪየ ፡ በከመ ፡ ጽድቅከ።
ወኢይትፈሥሑ ፡ ላዕሌየ ።



መዝሙር ፡ ፴፬ ።

ስለ ኤርምያስ ።

አቤቱ ፡ የሚበድሉኝን ፡ በድላቸው ፡ ፩
የሚዋጉኝንም ፡ ተዋጋቸው ።
ጥሩርና ፡ ጋሻ ፡ ያዝ ፤ ፪
እኔንም ፡ ለመርዳት ፡ ተነሥ ።
ሰይፍህን ፡ ምዘዝ ፡ ፫
የሚያሳድዱኝንም ፡ መንገዳቸውን ፡ ዝጋ ።
ነፍሴን ፡ መድኃኒትሽ ፡ እኔ ፡ ነኝ ፡ በላት ።
ነፍሴን ፡ የሚሹ ፡ ሁሉ ፡ ይፈሩ ፡ ይጐስቍሉም ፡ ፬
ክፋትን ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ የሚያስቡ ፡ ይፈሩ ፡
ወደ ፡ ኋላቸውም ፡ ይመለሱ ።
በነፋስ ፡ ፊት ፡ እንዳለ ፡ ትቢያ ፡ ይሁኑ ፡ ፭
የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ ያስጨንቃቸው ።
መንገዳቸው ፡ ዳጥና ፡ ጨለማ ፡ ይሁን ፡ ፮
የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ ያሳዳቸው ።
በከንቱ ፡ ያጠፉኝ ፡ ዘንድ ፡ ወጥመዳቸውን ፡ አጥምደውብኛልና ፤ ፯
ነፍሴንም ፡ በከንቱ ፡ አበሳጭተዋልና ።
ያላወቁት ፡ ወጥመድ ፡ ያጥምዳቸው ፡ ፰
ያጠመዱትም ፡ ወጥመድ ፡ ይያዛቸው ፤
በዚህ ፡ ወጥመድ ፡ ውስጥ ፡ ይውደቁ ።
ነፍሴ ፡ ግን በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ይላታል ፡ ፱
በማዳኑም ፡ ሐሤትን ፡ ታደርጋለች ።
አጥንቶቼ ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ ይሉሃል ፡ ፲
አቤቱ ፡ እንደ ፡ አንተ ፡ ማን ፡ ነው ?
ችግረኛውን ፡ ከቀማኛ ፡ እጅ ፡
ምስኪኑንና ፡ ድሀውንም ፡ ከነጣቂ ፡ እጅ ፡ ታድነዋለህና ።
የሐሰት ፡ ምስክሮች ፡ ተነሡብኝ ፡ ፲፩
የማላውቀውንም ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ መሰከሩ ።
ስለ ፡ በጎነቴ ፡ ክፋትን ፡ መለሱልኝ ፡ ፲፪
ነፍሴንም ፡ ተስፋ ፡ አሳጡአት ።
እኔስ ፡ እነርሱ ፡ በታመሙ ፡ ጊዜ ፡ ማቅ ፡ ለበስሁ ፡ ፲፫
ነፍሴንም ፡ በጾም ፡ አደከምኋት ።
ጸሎቴም ፡ ወደ ፡ ብብቴ ፡ ተመለሰ ።
ለወዳጄና ፡ ለወንድሜ ፡ እንደማደርገው ፡ አደረግሁ ፤ ፲፬
ለእናቱም ፡ እንደሚያለቅስ ፡ ራሴን ፡ ዝቅ ፡ ዝቅ ፡ አደረግሁ ።
ግፈኞች ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ተሰበሰቡ ፡ ደስም ፡ አላቸው ፤ ፲፭
እኔ ፡ ግን ፡ አላወቅሁም ፤
ተነጣጠቁኝ ፡ አልተዉኝምም ።
ፈተኑኝ ፡ በሣቅም ፡ ዘበቱብኝ ፡ ፲፮
ጥርሳቸውንም ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ አንቀጫቀጩ ።
አቤቱ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ ታይልኛለህ ? ፲፯
ነፍሴን ፡ ከክፉ ፡ ሥራቸው ፡
ብቸኝነቴንም ፡ ከአንበሶች ፡ አድናት ።
አቤቱ ፡ በታላቁ ፡ ጉባኤ ፡ ውስጥ ፡ እገዛልሃለሁ ፡ ፲፰
በብዙ ፡ ሕዝብ ፡ መካከልም ፡ አመሰግንሃለሁ ።
በግፍ ፡ የሚጠሉኝ ፡ በላዬ ፡ ደስ ፡ አይበላቸው ፡ ፲፱
በከንቱ ፡ የሚጠሉኝም ፡ በዓይናቸው ፡ አይጠቃቀሱብኝ ።
ለእኔ ፡ ሰላምን ፡ ይናገሩኛል ፤ ፳
በቍጣም ፡ ሽንገላን ፡ ይመክራሉ ።
አፋቸውንም ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ አላቀቁ ፡ ፳፩
እሰይ ፡ እሰይ ፡ ዓይናችን ፡ አየው ፡ ይላሉ ።
አቤቱ ፡ አንተ ፡ አየኸው ፡ ዝም ፡ አትበል ፤ ፳፪
አቤቱ ፡ ከእኔ ፡ አትራቅ ።
አምላኬ ፡ ጌታዬም ፡ ወደ ፡ ፍርዴ ፡ ተነሥ ፡ ፳፫
አቤቱ ፡ ፍርዴን ፡ አድምጥ ።
አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ እንደ ፡ ጽድቅህ ፡ ፍረድልኝ ፡ ፳፬
በላዬም ፡ ደስ ፡ አይበላቸው ።

፳፭ ወኢይበሉ ፡ በልቦሙ ፡ እንቋዕ ፡ እንቋዕ ፡ ላዕለ ፡ ነፍስየ ።
ወኢይበሉ ፡ ውኅጥናሁ ።
፳፮ ለይትኀፈሩ ፡ ወይኅሰሩ ፡ እለ ፡ ይትፌሥሑ ፡ በሕማምየ ።
ወይልበሱ ፡ ኀፍረተ ፡ ወኀሣረ ፡ እለ ፡ ያዐብዩ ፡ አፉሆሙ ፡ ላዕሌየ ።
፳፯ ለይትፌሥሑ ፡ ወይትሐሠዩ ፡ እለ ፡ ይፈቅድዋ ፡ ለጽድቅየ ።
ወይበሉ ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ፡ ዐቢይ ፡
እለ ፡ ይፈቅዱ ፡ ሰላመ ፡ ገብርከ ።
፳፰ ልሳንየ ፡ ያነብብ ፡ ጽድቀከ ። ወኵሎ ፡ አሚረ ፡ ስብሐቲከ ።

መዝሙር ፡ ፴፭ ።

በእንተ ፡ ርእሱ ።

፩ ይነብብ ፡ ኃጥእ ፡ በዘያስሕት ፡ ርእሶ ።
ወአልቦ ፡ ፍርሀተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቅድመ ፡ አዕይንቲሁ ።
፪ እስመ ፡ ጸልሐወ ፡ በልሳኑ ።
ሶበ ፡ ትረክቦ ፡ ኀጢአቱ ፡ ይጸልኣ ።
፫ ቃለ ፡ አፉሁ ፡ ዐመፃ ፡ ወጕሕሉት ።
ወኢፈቀደ ፡ ይለቡ ፡ ከመ ፡ ያሠኒ ።
፬ ወሐለየ ፡ ዐመፃ ፡ በውስተ ፡ ምስካቡ ።
ወቆመ ፡ በፍኖት ፡ እንተ ፡ በኵሉ ፡ ኢኮነት ፡ ሠናይተ ።
ወኢይትሀከያ ፡ ለእኪት ።
፭ እግዚኦ ፡ በሰማይ ፡ ሣህልከ ።
ወጽድቅከኒ ፡ እስከ ፡ ደመናት ።
፮ ወርትዕከኒ ፡ ከመ ፡ አድባረ እግዚአብሔር ።
ኰነኔከ ፡ ዕሙቅ ፡ ጥቀ ።
ሰብአ ፡ ወእንስሳ ፡ ታድኅን ፡ እግዚኦ ።

፯ ወበከመ ፡ አብዛኅከ ፡ ምሕረተከ ፡ እግዚኦ ።
ደቂቀ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ፡ ይትዌከሉ ፡ በታሕተ ፡ ክነፊከ ።
፰ ወይረውዩ ፡ እምጠለ ፡ ቤትከ ።
ወትሰቅዮሙ ፡ እምፈለገ ፡ ትፍሥሕትከ ።
፱ እስመ ፡ እምኀቤከ ፡ ነቅዐ ፡ ሕይወት ።
በብርሃንከ ፡ ንርአይ ፡ ብርሃነ ።
፲ ሰፋሕ ፡ ምሕረተከ ፡ እግዚኦ ፡ ላዕለ ፡ እለ ፡ የአምሩከ ።
ወጽድቀከኒ ፡ ለርቱዓነ ፡ ልብ ።
፲፩ ኢይምጽአኒ ፡ እግረ ፡ ትዕቢት ።
ወእደ ፡ ኃጥእ ፡ ኢይሁከኒ ።
፲፪ ህየ ፡ ይወድቁ ፡ ኵሎሙ ፡ ገበርተ ፡ አመፃ ።
ይሰደዱ ፡ ወኢይክሉ ፡ ቀዊመ ።

መዝሙር ፡ ፴፮ ።

ተማኅጸን ፡ ለኵሉ ።

፩ ኢትቅናዕ ፡ ላዕለ ፡ እኩያን ።
ወኢትቅናዕ ፡ ላዕለ ፡ ገበርተ ፡ ዐመፃ ።
፪ እስመ ፡ ከመ ፡ ሣዕር ፡ ፍጡነ ፡ ይየብሱ ።
ወከመ ፡ ሐመልማለ ፡ ሐምል ፡ ፍጡነ ፡ ይወድቁ ።
፫ ተወከል ፡ በእግዚአብሔር ፡ ወግበር ፡ ሠናየ ።
ወያኅድረከ ፡ ዲበ ፡ ምድር ።
ወይረዕየከ ፡ ዲበ ፡ ብዕላ ።
፬ ተፈግሕ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ወይሁበከ ፡ ስእለተ ፡ ልብከ ።
፭ ክሥት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ፍኖተከ ።
ተወከል ፡ ቦቱ ፡ ወውእቱ ፡ ይገብር ፡ ለከ ።
፮ ወያመጽእ ፡ ከመ ፡ ብርሃን ፡ ለጽድቅከ ።
ወፍትሕከኒ ፡ ከመ ፡ መዓልት ።



በልባቸው ፡ እሰይ ፡ እሰይ ፡ ነፍሳችንን ፡ ደስ ፡ ይበላት ፡ ፳፭
ዋጥነውም ፡ አይበሉ ።
በመከራዬ ፡ ደስ ፡ የሚላቸው ፡ ይፈሩ ፡ ፳፮
በአንድነትም ፡ ይጐስቈሉ ።
በእኔ ፡ ላይ ፡ የሚታበዩ ፡ ዕፍረትንና ፡ ጕስቍልናን ፡ ይልበሱ ።
ጽድቄን ፡ የሚወዱአት ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ፡ ፳፯
ሐሤትንም ፡ ያድርጉ ።
የባሪያውን ፡ ሰላም ፡ የሚወድ ፡ እግዚአብሔር ፡
ዘወትር ፡ ታላቅ ፡ ይሁን ፡ ይበሉ ።
አንደበቴ ፡ ሁል ፡ ጊዜም ፡ ጽድቅህን ፡ ፳፰
ምስጋናህንም ፡ ይናገራል ።

መዝሙር ፡ ፴፭ ።

ስለ ራሱ ።

ኃጢአተኛ፡በራሱ ፡ የሚያስት ፡ ነገርን ፡ ይናገራል ፡ ፩
የእግዚአብሔርም ፡ ፍርሃት ፡ በዓይኖቹ ፡ ፊት ፡ የለም ።
በአንደበቱ ፡ ሸንግሎአልና ፡ ፪
ኃጢአቱ ፡ ባገኘችው ፡ ጊዜ ፡ ይጠላታል ።
የአፉ ፡ አነጋገር ፡ ግፍና ፡ ሽንገላ ፡ ነው ፡ ፫
ማስተዋልን ፡ በጎ ፡ ማድረግንም ፡ ተወ ።
በመኝታው ፡ ላይ ፡ ዓመፃን ፡ አሰበ ፡ ፬
መልካም ፡ ባልሆነች ፡ መንገድ ፡ ቆሞአል ፡
ክፋትን ፡ አያልፋትም ።
አቤቱ ፡ ምሕረትህ ፡ በሰማይ ፡ ነው ፡ ፭
እውነትህም ፡ ወደ ፡ ደመናት ፡ ትደርሳለች ።
ጽድቅህም ፡ እንደ እግዚአብሔር ፡ ተራሮች ፡ ፮
የመጠቆች ፡ ናት ።
ፍርድህም ፡ እጅግ ፡ ጥልቅ ፡ ናት ፡
አቤቱ ፡ ሰውንና ፡ እንስሳን ፡ ታድናለህ ።

አቤቱ ፡ ምሕረትህን ፡ እንዴት ፡ አበዛህ ፡ ፯
የሰው ፡ ልጆች ፡ በክንፎችህ ፡ ጥላ ፡ ይታመናሉ ።
ከቤትህ ፡ ጠል ፡ ይጠግባሉ ፡ ፰
ከተድላህም ፡ ፈሳሽ ፡ ታጠጣቸዋለህ ።
የሕይወት ፡ ምንጭ ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡ ነውና ፡ ፱
በብርሃንህ ፡ ብርሃንን ፡ እናያለን ።
ምሕረትህን ፡ በሚያውቁህ ፡ ላይ ፡ ፲
ጽድቅህንም ፡ ልባቸው ፡ በቀና ፡ ላይ ፡ ዘርጋ ።
የትዕቢት ፡ እግር ፡ አይምጣብኝ ፡ ፲፩
የኃጢአተኞችም ፡ እጅ ፡ አያውከኝ ።
ዓመፃን ፡ የሚያደርጉ ፡ ሁሉ ፡ ከዚያ ፡ ወደቁ ፡ ፲፪
ወድቀዋል ፡ መቆምም ፡ አይችሉም ።

መዝሙር ፡ ፴፮ ።

ተማኅጸና ፡ ምከር ፡ ለሁሉ ።

በክፉዎች ፡ ላይ ፡ አትቅና ፡ ፩
ዓመፃንም ፡ በሚያደርጉ ፡ ኀሳብ ፡ አትማረክ ፡
እንደ ፡ ሣር ፡ ፈጥነው ፡ ይደርቃሉና ። ፪
እንደ ፡ ቅጠልም ፡ ይረግፋሉና ።
በእግዚአብሔር ፡ ታመን ፡ መልካምን ፡ አድርግ ፡ ፫
በምድርም ፡ ተቀመጥ ፡ ታምነህም ፡ ተሰማራ ።
በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ይበልህ ፡ ፬
የልብህንም ፡ ፍላጎት ፡ ይሰጥሃል ።
መንገድህን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አደራ ፡ ስጥ ፡ ፭
በእርሱም ፡ ታመን ፡ እርሱም ፡ ያደርግልሃል ።
ጽድቅህን ፡ እንደ ፡ ብርሃን ፡ ፮
ፍርድህንም ፡ እንደ ፡ ቀትር ፡ ሰዓት ፡ ያመጣል ።

፯ ግነይ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ወተጸመዶ ።
ወኢትቅናዕ ፡ ላዕለ ፡ ዘይዴሎ ፡ በሕይወቱ ።
ወላዕለ ፡ ሰብእ ፡ ዘይገብር ፡ ዐመፃ ።
፰ ኅድጋ ፡ ለመዓት ፡ ወግድፋ ፡ ለቍጥዓ ።
ወኢትቅናዕ ፡ ከመ ፡ ታሕስም ።
፱ እስመ ፡ እለ ፡ ያሐስሙ ፡ ይሤረዉ ።
ወእለሰ ፡ ይትዔገሥዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እሙንቱ ፡
ወይረስዋ ፡ ለምድር ።
፲ ወዓዲ ፡ ኅዳጠ ፡ ኢይሄሉ ፡ እንከ ፡ ኃጥእ ።
ተኀሥሥ ፡ ወኢትረክብ ፡ መካኖ ።
፲፩ የዋሃንሰ ፡ ይወርስዋ ፡ ለምድር ።
ወይትፌሥሑ ፡ በብዙኅ ፡ ሰላም ።
፲፪ ያስተሐይጾ ፡ ኃጥእ ፡ ለጻድቅ ፡ ወየሐቂ ፡ ስነኒሁ ፡
ላዕሌሁ ።
፲፫ ወእግዚአብሔርሰ ፡ ይሥሕቆ ።
እስመ ፡ ያቀድም ፡ አእምሮ ፡ ከመ ፡ በጽሐ ፡ ዕለቱ ።
፲፬ ሰይፎሙ ፡ መልኁ ፡ ኃጥአን ። ወወሰቁ ፡ ቀስቶሙ ።
ከመ ፡ ይቅትልዎ ፡ ለነዳይ ፡ ወለምስኪን ።
ወከመ ፡ ይርግዝዎሙ ፡ ለርቱዓነ ፡ ልብ ።
፲፭ ሰይፎሙ ፡ ይባእ ፡ ውስተ ፡ ልቦሙ ።
ወይትቀጥቀጥ ፡ አቅስስቲሆሙ ።
፲፮ ይኄይስ ፡ ኅዳጥ ፡ ዘበጽድቅ ።
እምብዙኅ ፡ ብዕለ ፡ ኃጥአን ።
፲፯ እስመ ፡ ይትቀጠቀጥ ፡ ኀይሎሙ ፡ ለኃጥአን ።
ያጸንዖሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለጻድቃን ።
፲፰ ወየአምር ፡ እግዚአብሔር ፡ ፍኖተ ፡ ንጹሓን ።
ወለዓለም ፡ ውእቱ ፡ ርስቶሙ ።
፲፱ ወኢይትኀፈሩ ፡ በመዋዕለ ፡ እኩይት ።
ወይጸግቡ ፡ በመዋዕለ ፡ ረኃብ ።

፳ ወኃጥአንሰ ፡ ይትሀጐሉ ፡
ጸላእቱሰ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ሶበ ፡ ከብሩ ፡ ወተለዐሉ።
የኀልቁ ፡ ወይጠፍኡ ፡ ከመ፡ ጢስ ።
፳፩ ይትሌቃሕ ፡ ኃጥእ ፡ ወኢይፈዲ ።
ጻድቅሰ ፡ ይምሕር ፡ ወይሁብ ።
፳፪ እስመ ፡ እለ ፡ ይባርክዎ ፡ ይወርስዋ ፡ ለምድር ።
ወእለሰ ፡ ይረግሙ ፡ ይሤረዉ ።
፳፫ እምኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያጸንዖ ፡ ሑረቱ ፡ ለሰብእ ።
ለዘይፈቅድ ፡ ፍኖቶ፡ ፈድፋደ ።
፳፬ እመኒ ፡ ወድቀ ፡ ኢይደነግፅ ።
እስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ይሰውቆ ፡ እዴሁ ።
፳፭ ወርዘውኩኒ ፡ ወረሣእኩ ።
ወጻድቅሰ ፡ ዘይትገደፍ ፡ ኢርኢኩ ።
ወዘርዖኒ ፡ ኢይጼንስ ፡ እክለ ።
፳፮ ወኵሎ ፡ አሚረ ፡ ይምሕር ፡ ወይሌቅሕ ።
ወዘርዑኒ ፡ ውስተ ፡ በረከት ፡ ይሄሉ ።
፳፯ ተገሐሥ ፡ እምእኩይ ፡ ወግበር ፡ ሠናየ ።
ወትነብር ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ።
፳፰ እስመ ፡ ጽድቀ ፡ ያፈቅር ፡ እግዚአብሔር ።
ወኢይገድፎሙ ፡ ለጻድቃን ፡
ወለዓለም ፡ የዐቅቦሙ ።
ወይትቤቀል ፡ ሎሙ ፡ ለንጹሓን ።
ወይሤሩ ፡ ዘርዖሙ ፡ ለኃጥአን ።
፳፱ ጻድቃንሰ ፡ ይወርስዋ ፡ ለምድር ።
ወይነብሩ ፡ ውስቴታ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ።
፴ አፉሁ ፡ ለጻድቅ ፡ ይትሜሀር ፡ ጥበበ ።
ወልሳኑ ፡ ይነብብ ፡ ጽድቀ ።
፴፩ ወሕገ ፡ አምላኩ ፡ ውስተ ፡ ልቡ ።
ወኢይድኅፅ ፡ ሰኰናሁ ።



ለእግዚአብሔር ተገዛ ፡ ተስፋም ፡ አድርገው ፡ ፯
ለጊዜው ፡ መንገዱ ፡ በቀናችለትና ፡ ጠማምነትን ፤
በሚያደርግ ፡ ሰው ፡ አትቅና ።
ከቍጣ ፡ ራቅ ፡ መዓትንም ፡ ተው ፤ ፰
እንዳትበድል ፡ አትቅና ።
ክፉ ፡ አድራጊዎች ፡ ይጠፉሉና ፡ ፱
በእግዚአብሔር ፡ ተስፋ ፡ የሚያደርጉ ፡ ግን ፡
እነርሱ ፡ ምድርን ፡ ይወርሳሉ ።
ጥቂት ፡ ስንኳ ፡ ኃጢአተኛ ፡ አይኖርም ፡ ፲
ትፈልገዋለህ ፡ በታውን ፡ አታገኘውም ።
ደኃኖች ፡ ግን ፡ ምድርን ፡ ይወርሳሉ ፡ ፲፩
በብዙም ፡ ሰላም ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
ኃጢአተኛ ፡ ጻድቁን ፡ ይመለካከተዋል ፡ ፲፪
ጥርሱንም ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ያንገጫግጫል ።
እግዚአብሔርስ ፡ ይሥቅበታል ፡ ፲፫
ቀኑ ፡ እንደሚደርስ ፡ አይቶአልና ።
ድሀውንና፡ ችግረኛውን ፡ ይጥሉ ፡ ዘንድ ፡ ፲፬
ልበ ፡ ቅኖችንም ፡ ይወጉ ፡ ዘንድ ፤
ኃጢአተኞች ፡ ሰይፋቸውን ፡ መዘዙ ፡
ቀስታቸውንም ፡ አነጣጠሩ ።
ሰይፋቸው ፡ ወደ ፡ ልባቸው ፡ ይግባ ፡ ፲፭
ቀስታቸውም ፡ ይሰበር ።
ለጻድቅ ፡ ያለው ፡ የው ፡ ጥቂት ፡ ነገር ፡ ፲፮
ከብዙ ፡ የኃጢአተኞች ፡ ሀብት ፡ ይበልጣል ።
የኀጥኣን ፡ ክንድ ፡ ትሰበራለችና ፡ ፲፯
እግዚአብሔር ፡ ግን፡ጻድቃንን ፡ ይደግፋቸዋል ።
የንጹሐንን ፡ መንገድ ፡እግዚአብሔር ያውቃል ፡ ፲፰
ርስታቸውም ፡ ለዘላለም ፡ ነው ።
በክፉ ፡ ዘመንም ፡ አያፍሩም ፡ ፲፱
በራብ ፡ ዘመንም ፡ ይጠግባሉ ።

ኃጥአን ፡ ግን ፡ ይጠፋሉ ፡ ፳
የእግዚአብሔር ፡ ጠላቶች ፡ በክበሩና ፡ ከፍ ፡ከፍ ፡
ባሉ ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ጢስ ፡ ይጠፋሉ ።
ኃጢአተኛ ፡ ይበደራል ፡ አይከፍልም ፡ ፳፩
ጻድቅ ፡ ግን ፡ ይራራል ፡ ይሰጣልም ።
እርሱን ፡ የሚባርኩት ፡ ምድርን ፡ ይወርሳሉና ፤ ፳፪
የሚረግሙት ፡ ግን ፡ ይጠፋሉ ።
የጻድቅ ፡ አካሄድ ፡ከእግዚአብሔር ፡ዘንድ ፡ ይጸናል ፡ ፳፫
መንገዱንም ፡ ይባርክለታል ።
ቢወድቅም ፡ ጉዳት ፡ አይደርስበትም ፤ ፳፬
እግዚአብሔር ፡ እጁን ፡ ይዞ ፡ ይደግፈዋልና ።
ጐልምሼ ፡ እስካረጀሁ ፡ ድረስ ፡ ጻድቅ ፡ ሲጣል ፡ ፳፭
ዘሩም ፡ እህል ፡ ሲለምን ፡ አላየሁም ።
ሁል ፡ ጊዜ ፡ ይራራል ፡ ያበድርማል ፡ ፳፮
ዘሩም ፡ በበረከት ፡ ይኖራል ።
ከክፉ ፡ ራቅ ፡ መልካምንም ፡ አድርግ ፡ ፳፯
ለዘላለምም ፡ ትኖራለህ ።
እግዚአብሔር ፡ ፍርድን ፡ ይወዳልና ፡ ፳፰
ቅዱሳኑንም ፡ አይጥላቸውምና ፤
ለዘላለምም ፡ ይጠብቃቸዋል ፡
ለንጹሐንም ፡ ይበቀልላቸዋል ፤
የኃጥአን ፡ ዘር ፡ ግን ፡ ይጠፋል ።
ጻድቃን ፡ ምድርን ፡ ይወርሳሉ ፡ ፳፱
በእርስዋም ፡ ለዘላለም ፡ ይኖራሉ ።
የጻድቅ ፡ አፍ ፡ ጥበብን ፡ ያስተምራል ፡ ፴
አንደበቱም ፡ ፍርድን ፡ ይናገራል ።
የአምላኩ ፡ ሕግ ፡ በልቡ ፡ ውስጥ ፡ ነው ፡ ፴፩
በእርምጃውም ፡ አይሰናከልም ።

፴፪ ያስተሐይጾ ፡ ኃጥእ ፡ ለጻድቅ ።
ወይፈቅድ ፡ ይቅትሎ ።
፴፫ ወኢየኀድጎ ፡ እግዚአብሔር ፡ ውስተ ፡ እደዊሁ ።
ወኢይመውዖ ፡ ሶበ ፡ ይትዋቀስ ።
፴፬ ተዐገሥ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ወዕቀብ ፡ ፍኖቶ ።
ወያዐብየከ ፡ ከመ ፡ ትረሳ ፡ ለምድር ።
ወትሬኢ ፡ ከመ ፡ ይሤረዉ ፡ ኃጥአን ።
፴፭ ርኢክዎ ፡ ለኃጥእ ፡ ዐብየ ፡ ወተለዓለ ፡ ከመ ፡ አርዘ ፡ ሊባኖስ ።
፴፮ ወሶበ ፡ እገብእ ፡ ኃጣእክዎ ።
ኀሠሥኩ ፡ ወኢረከብኩ ፡ መካኖ ።
፴፯ ዕቀብ ፡ የዋሃተ ፡ ወትሬኢ ፡ ጽድቀ ።
እስመ ፡ ቦቱ ፡ ተረፈ ፡ ብእሲ ፡ ሰላም ።
፴፰ ወበማዕዶንሰ ፡ ይሤረዉ ።
ወይሤረዉ ፡ ትራፋቲሆሙ ፡ ለኃጥአን ።
፴፱ መድኃኒቶሙ ፡ ለጻድቃን ፡ እምኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡
ወተቀዋሚሆሙ ፡ ውእቱ ፡ በጊዜ ፡ ምንዳቤሆሙ ።
፵ ይረድኦሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወያድኅኖሙ ።
ወያነግፎሙ ፡ እምእደ ፡ ኃጥአን ።
ወያድኅኖሙ ፡ እስመ ፡ ተወከሉ ፡ ቦቱ ።

መዝሙር ፡ ፴፯ ።

በእንተ ፡ ርእሱ ፡ አመ ፡ በሰፎ ፡ ሳሚ ፡ ወልደ ፡ ጌራ ።

፩ እግዚኦ ፡ በመዓትከ ፡ ኢትቅሥፈኒ ።
ወበመቅሠፍትከ ፡ ኢትገሥጸኒ ።
፪ እስመ ፡ አሕጻከ ፡ ይገዝጸኒ ።
ወአጽናዕከ ፡ እዴከ ፡ ላዕሌየ ።
፫ ወአልቦ ፡ ፈውስ ፡ ለሥጋየ ፡ እምገጸ ፡ መዓትከ ።
ወአልቦ ፡ ሰላም ፡ ለአዕፅምትየ ፡ እምገጸ ፡ ኃጢአትየ ።

፬ እስመ ፡ ኖኀ ፡ እምሥእርተ ፡ ርእስየ ፡ ጌጋይየ ።
ከመ ፡ ጾር ፡ ክቡድ ፡ ከብደ ፡ ላዕሌየ ።
፭ ጼዓ ፡ ወበኍቡኆ ፡ አዕፅምትየ ፡ እምገጸ ፡ አበድየ ።
፮ ሐርተምኩ ፡ ወተቀጻዕኩ ፡ ለዝሉፉ ።
ወኵሎ ፡ አሚረ ፡ ትኩዝየ ፡ አንሶሱ ።
፯ እስመ ፡ ጸግበት ፡ ጽዕለተ ፡ ነፍስየ ።
ወኀጣእኩ ፡ ፈውሰ ፡ ለሥጋየ ።
፰ ደወይኩ ፡ ወሐመምኩ ፡ ፈድፋደ ።
ወእኆሥዕ ፡ እምኀዘነ ፡ ልብየ ።
፱ በቅድሜከ ፡ ኵሉ ፡ ፍትወትየ ።
ወገዓርየኒ ፡ ኢይትኀባእ ፡ እምኔከ ።
፲ ልብየኒ ፡ ደንገጸኒ ፡ ወኀይልየኒ ፡ ኀደገኒ ።
ወብርሃነ ፡ አዕይንትየኒ ፡ ለከወኒ ።
፲፩ አዕርክትየኒ፡ወቢጽየኒ፡ዕድወ፡ ኮኑኒ፡ሮዱኒ፡ ወደበዩኒ ።
ወአዝማድየኒ ፡ ቀብጹኒ ፡ ወተናከሩኒ ።
፲፪ ወተኃየሉኒ ፡ እለ ፡ የኀሥሥዋ ፡ ለነፍስየ ።
ወእለኒ ፡ ይፈቅዱ ፡ ሕማምየ ፡ ነበቡ ፡ ከንቶ ።
ወኵሎ ፡ አሚረ ፡ ይመክሩ ፡ በቍጽር ፡ ያመንስዉኒ ።
፲፫ ወአንሰ ፡ ከመ ፡ ጽሙም ፡ ዘኢይሰምዕ ።
ወከመ ፡ በሃም ፡ ዘኢይከሥት ፡ አፉሁ ።
ወኮንኩ ፡ ከመ ፡ ብእሲ ፡ ዘኢይሰምዕ ።
፲፬ ወከመ ፡ ዘኢይክል ፡ ተናግሮ ፡ በአፉሁ ።
፲፭ እስመ ፡ ኪያከ ፡ ተወከልኩ ፡ እግዚኦ ።
አንተ ፡ ስምዐኒ ፡ እግዚኦ ፡ አምላኪየ ።
፲፮ እስመ ፡ እቤ ፡ ኢትረስየኒ ፡ ስላተ ፡ ጸላእየ ።
ወእመኒ ፡ ድኅፀ ፡ ሰኰናየ፡ያዐብዩ፡አፉሆሙ፡ላዕሌየ ።
፲፯ እስመ ፡ ሊተሰ ፡ አጽንሑኒ ፡ ይቅሥፉኒ ።
ወቍስልየኒ ፡ ቅድሜየ ፡ ውእቱ ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ።



ኃጢአተኛ ፡ ጻድቁን ፡ ይመለከተዋል ፡ ፴፪
ሊገድለውም ፡ ይወዳል ።
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ በእጁ ፡ አይጥለውም ፡ ፴፫
በተፋረደው ፡ ጊዜ ፡ አያሸንፈውም ።
እግዚአብሔርን ፡ደጅ ፡ ጥና ፡ መንገዱንም ፡ ጠብቅ ፡ ፴፬
ምድርንም፡ትወርስ፡ ዘንድ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደርግሃል ፡
ኃጢአተኞችም ፡ ሲጠፉ ፡ ታያለህ ።
ኃጥእን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብሎ ፡ ፴፭
እንደ ፡ ሊባኖስ ፡ ዝግባም ፡ ለምልሞ ፡ አየሁት ።
ብመለስ ፡ ግን ፡ አጣሁት ፡ ፴፮
ፈለግሁት ፡ በቦታውንም ፡ አላገኘሁም ።
ቅንነትን ፡ ጠብቅ ፡ ጽድቅንም ፡ ተመልከት ፡ ፴፯
ለሰላም ፡ ሰው ፡ ተስፋ ፡ አለውና ።
በደለኞች ፡ በአንድነት ፡ ይጠፋሉ ፡ ፴፰
የኃጢአተኞች ፡ ተስፋ ፡ ይጠፋል ።
የጻድቃን፡መድኃኒታቸው፡ ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ነው፡ ፴፱
በመከራቸውም ፡ ጊዜ ፡ መጠጊያቸው ፡ እርሱ ፡ ነው ።
እግዚአብሔር ፡ይረዳቸዋል ፡ ያድናቸዋልም ፡
ከኃጢአተኞችም ፡ እጅ ፡ ያወጣቸዋል ፡
ያድናቸዋልም ፡ በእርሱ ፡ ታምነዋልና ።

መዝሙር ፡ ፴፯ ።

ስለራሱ ፡ የጌራ ፡ ልጅ ፡ ሳሚ ፡ በሰደበው ፡ ጊዜ ።

አቤቱ ፡ በቍጣህ ፡ አትቅሠፈኝ ፡ ፩
በመዓትህም ፡ አትገሥጸኝ ።
ፍላጾችህ ፡ ወግተውኛልና ፡ ፪
እጅህንም ፡ አክብደህብኛልና ።
ከቍጣህ፡የተነሣ፡ሰውነቴ፡ጤና፡የለውም፡ከኃጢአቴም፡ ፫
የተነሣ ፡ ለአጥንቶቼ ፡ ሕይወት ፡ አይኖራቸውም ።

ኃጢአቴ ፡ ከራሴ ፡ በላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ብሎአልና ፡ ፬
እንደ ፡ ከባድ ፡ ሸክምም ፡ በላዬ ፡ ተጭኗልና ።
ከስንፍናዬ ፡ የተነሣ ፡ ቍስሌ ፡ ሸተተ ፡ በሰበሰም ። ፭
እጅግ ፡ ጕስቁልሁ ፡ ተዋረድሁም ፡ ፮
ሁል ፡ ጊዜም ፡ በትካዜ ፡ እመላለሳለሁ ።
ነፍሴ ፡ ስድብን ፡ ተሞልታለችና ፡ ፯
ለሥጋዬም ፡ ጤና ፡ የላትምና ።
ታመምሁ ፡ እጅግም ፡ ተቸገርሁ ፡ ፰
ከልቤ ፡ ውዝዋዜም ፡ የተነሣ ፡ ጮኽሁ ።
አቤቱ ፡ ፈቃዴ ፡ ሁሉ ፡ በፊትህ ፡ ነው ፡ ፱
ጭንቀቴም ፡ ከአንተ ፡ አይሰወርም ።
ልቤ ፡ ደነገጠብኝ ፡ ኃይሌም ፡ ተለየችኝ ፡ ፲
የዓይኖቼም ፡ ብርሃን ፡ ፈዘዘ ።
ወዳጆቼም ፡ ባልንጀሮቼም ፡ ከቍስሌ ፡ ፊት ፡ ሸሹ ፡ ፲፩
ዘመዶቼም ፡ ርቀው ፡ ቆሙ ።
ነፍሴንም ፡ የሚፈልጓት ፡ በረቱብኝ ፡ ፲፪
በመከራዬም ፡ የሚደሰቱ ፡ ከንቱን ፡ ተናገሩ ፡
ሁል ፡ ጊዜም ፡ በሽንገላ ፡ ይመክራሉ ።
እኔ ፡ ግን ፡ እንደማይሰማ ፡ ደንቆሮ ፡ ፲፫
በአፉም ፡ መናገር ፡ እንደማይችል ፡ ዲዳ ፡ ሆንሁ ።
እንደማይሰማና ፡ በአንደበቱም ፡ መልስ ፡ ፲፬
እንደማይሰጥ ፡ ሰው ፡ ሆንሁ ።
አቤቱ ፡ በአንተ ፡ ታምኛለሁና ፡ ፲፭
አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ አንተ ፡ ትሰማኛለህ ።
ጠላቶቼ ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ደስ ፡ እንዳይላቸው ፡ ፲፮
ብያለሁና ፡ እግሮቼም ፡ ቢሰናከሉ ፡ ራሳቸውን ፡
በእኔ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደርጋሉ ።
እኔስ ፡ ወደ ፡ ማንከስ ፡ ተቃርቤአለሁ ፡ ፲፯
ቍስሌም ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ በፊቴ ፡ ነውና ።

፲፰ ወእነግር ፡ ጌጋይየ ፡ ወእቴክዝ ፡ በእንተ ፡ ኀጢአትየ ።
፲፱ ጸላእትየስ ፡ ሕያዋን ፡ ወይኄይሉኒ ።
ወበዝኁ ፡ እለ ፡ በዐመፃ ፡ ይጸልኡኒ ።
እለ ፡ ይፈድዩኒ ፡ እኪተ ፡ ህየንተ ፡ ሠናይት ።
፳ ወያስተዋድዩኒ ፡ በተሊወ ፡ ጽድቅ ።
ወገደፉ ፡ እኅዋሆሙ ፡ ከመ ፡ በድን ፡ ርኩስ ።
፳፩ አንተ ፡ ኢትግድፈኒ ፡ እግዚኦ ፡ አምላኪየ ፡ ወኢ
ትርኃቅ ፡ እምኔየ ።
፳፪ ወነጽር፡ውስተ፡ረዲኤትየ፡እግዚኦ፡አምላኪ፡ መድኃኒትየ

መዝሙር ፡ ፴፰ ።

በእንተ ፡ ርእሱ ፡ አመ ፡ ሰደዶ ፡ ሳኦል ።

፩ ዕቤ ፡ አዐቅብ ፡ አፉየ ፡ ከመ ፡ ኢይስሐት ፡ በልሳንየ ።
ወአንበርኩ ፡ ዐቃቤ ፡ ለአፉየ ።
ሶበ ፡ ይትቃወሙኒ ፡ ኃጥአን ፡ ቅድሜየ ።
፪ ተጸመምኩ ፡ ወአትሐትኩ ፡ ርእስየ ።
ወአርመምኩ ፡ ለሠናይ ።
ወተሐደሰኒ ፡ ቍስልየ ።
፫ ወሞቅኒ ፡ ልብየ ፡ በውስጥየ ።
ወነደ ፡ እሳት ፡ እምአንብቦትየ ።
፬ ወአቤ ፡ በልሳንየ ፡ ንግረኒ ፡ እግዚኦ ፡ ደኃሪትየ ።
ምንት ፡ እማንቱ ፡ ኍልቆን ፡ ለመዋዕልየ ።
ከመ ፡ እእምር ፡ ለምንት ፡ እጼነር ፡ አነ ።
፭ ናሁ ፡ ብሉያተ ፡ ረሰይኮን ፡ ለመዋዕልየ ።
ወአካልየኒ ፡ ወኢከመ ፡ ምንት ፡ በቅድሜከ ።
ወባሕቱ ፡ ከንቱ ፡ ኵሉ ፡ ደቂቀ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ።
ወከመ ፡ ጽላሎት ፡ ያንሶሱ ፡ ኵሉ ፡ ሰብእ ።
፮ ወባሕቱ ፡ ከንቶ ፡ ይትሀወኩ ።
ይዘግቡ ፡ ወኢየአምሩ ፡ ለዘየስተጋብኡ ።
፯ ወይእዜኒ ፡ መኑ ፡ ተስፋየ ፡ አኮኑ ፡እግዚአብሔር ።
ወትዕግሥትየኒ ፡ እምኀቤከ ፡ ውእቱ ።
፰ ወእምኵሉ ፡ ኀጢአትየ ፡ አድኅንኒ ።
ወረሰይከኒ ፡ ጽእለተ ፡ ለአብዳን ።
ተጸመምኩ ፡ ወኢከሠትኩ ፡ አፉየ ።
፱ እስመ ፡ አንተ ፡ ፈጠርከኒ ።
፲ አርኅቅ ፡ እምኔየ ፡ መቅሠፍተከ ።
እስመ ፡ እምጽንዐ ፡ እዴከ ፡ ኀለቁ ፡ አነ ።
፲፩ በተግሣጽከ ፡ በእንተ ፡ ኀጢአቱ ፡ ተዛለፍኮ ፡ ለሰብእ።
ወመሰውካ ፡ ከመ ፡ ሣሬት ፡ ለነፍሱ ።
ወባሕቱ ፡ ከንቱ ፡ ይትሀወኩ ፡ ኵሉ ፡ ሰብእ ።
፲፪ ስምዐኒ ፡ እግዚኦ ፡ ጸሎትየ ፡ ወስእለትየ ።
ወአጽምዐኒ ፡ አንብዕየ ፡ ወኢትጸመመኒ ።
እስመ ፡ ፈላሲ ፡ አነ ፡ ውስተ ፡ ምድር ።
ወነግድ ፡ ከመ ፡ ኵሉ ፡ አበውየ ።
ሥኅተኒ ፡ ከመ ፡ አዕርፍ ።
፲፫ ዘእንበለ ፡ እሑር ፡ ኀበ ፡ ኢይገብእ ።

መዝሙር ፡ ፴፱ ።

በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ ጸኒሐ ፡ ጸናሕክዎ ፡ ለእግዚአብሔር ።
ሰምዐኒ ፡ ወተመይጠኒ ።
ወሰምዐኒ ፡ ቃለ ፡ ስእለትየ ።
፪ ወአውፅአኒ ፡ እምዐዘቅተ ፡ ሕርትምና ።
ወእምጽቡር ፡ ዐምዓም ።
ወአቀሞን ፡ ውስተ ፡ ኰኵሕ ፡ ለእገርየ ።
ወአጽንዖን ፡ ለመከየድየ ።



በደሌን ፡ እናገራለሁ ፡ ፲፰
ስለ ፡ ኃጢአቴም ፡ እተክዛለሁ ።
ጠላቶቼ ፡ ሕያዋን ፡ ናቸው ፡ ይበረቱብኝማል ፡ ፲፱
በከንቱም ፡ የሚጠሉኝ ፡ በዙ ።
ጽድቅን ፡ ስለ ፡ ተከተልሁ ፡ ፳
በበጎ ፡ ፋንታ፡ ክፉን ፡ ይመልሱልኛል ፡ ይጣሉኛልም ።
አቤቱ ፡ አንተ ፡ ግን ፡ አትጣለኝ ፡ ፳፩
አምላኬ ፡ ከኔ ፡ አትራቅ ።
አቤቱ ፡ መድኃኒቴ ፡ እኔን ፡ ለመርዳት ፡ ፍጠን ። ፳፪

መዝሙር ፡ ፴፰ ።

ስለ ፡ ራሱ ፡ ሳኦል ፡ ባሳደደው ፡ ጊዜ ።

በአንደበቴ ፡ እንዳልሳሳት ፡ አንደበቴን ፡ እጠብቃለሁ ። ፩
ኃጢአተኛ ፡ በፊቴ ፡ በተቃወመኝ ፡ ጊዜ ፡
በአፌ ፡ ላይ ፡ ጠባቂ ፡ አኖራለሁ ።
ከዝምታ ፡ የተነሣ ፡ እንደ ፡ ዲዳ ፡ ሆንሁ ፡ ፪
ለበጎ ፡ ነገር ፡ እንኳ ፡ ዝም ፡ አልሁ ፡
ቍስሌም ፡ ታደሰብኝ ።
ልቤም ፡ በውስጤ ፡ ሞቀብኝ ፡ ፫
ከማሰቤም ፡ የተነሣ ፡ እሳት ፡ ነደደ ፡
በአንደበቴም ፡ ተናገርሁ ።
የዘመኔ ፡ ቍጥሮች ፡ ምን ፡ ያህል ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ ፬
እኔስ ፡ምን፡ያህል፡ወደ፡ኋላ፡እንደምቀይ፤አውቅ፡ዘንድ ፡
አቤቱ፡ ፍጻሜዬን ፡ አስታውቀኝ ።
እነሆ ፡ ዘመኖቼን ፡ አስረጀሃቸው ፡ ፭
አካሌም ፡ በፊትህ ፡ እንደ ፡ ኢምንት ፡ ነው ፡
ሕያው ፡ የሆነ ፡ ሰው፡ሁሉ ፡ በእውነት ፡ ከንቱ ፡ ነው ።
በከንቱም ፡ ይታወካል ፡ ፮
በእውነት ፡ ሰው ፡ እንደ፡ጥላ ፡ ይመላለሳል ፡
ያከማቻል ፡ ለማን ፡ እንደሚያከማችም ፡ አያውቅም ።
አሁንስ፡ ተስፋዬ፡ማን፡ነው?እግዚአብሔር ፡ አይደለምን? ፯
ትዕግሥቴም ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡ ነው ።
ከኃጢአቴ ፡ ሁሉ ፡ አድነኝ ፡ ፰
ለሰነፎችም ፡ መዘበቻ ፡ አታድርገኝ ።
አንተ ፡ ሠርተኸኛልና ፡ ፱
ዝም ፡ አልሁ ፡ አፌንም ፡ አልከፈትሁም ።
መቅሠፍትህን ፡ ከእኔ ፡ አርቅ ፡ ፲
ከእጅህ ፡ ብርታት ፡ የተነሣ ፡ አልቄአለሁና ።
በተግሣጽህ ፡ ስለ ፡ ኃጢአቱ ፡ ሰውን ፡ ዘለፍኸው ፡ ፲፩
ነፍሱም ፡ እንደ ፡ ሸረሪት ፡ ድር ፡ ቀልቃለች ፤
በእውነት ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ከንቱ ፡ ነው ።
አቤቱ ፡ ጸሎቴን ፡ ስማ ፡ ጩኸቴንም ፡ አድምጥ ፡ ፲፪
ልቅሶዬንም ፡ ቸል ፡ አትበለኝ ፤
እኔ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ መጻተኛ ፡ ነኝና ፡
እንደ ፡ አባቶቼም ፡ እንግዳ ፡ ነኝና ።
ወደማልመለስበት ፡ ሳልሄድ ፡ ዐርፍ ፡ ዘንድ ፡ ተወኝ ። ፲፫

መዝሙር ፡ ፴፱ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

ቆይቼ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ደጅ ፡ ጠናሁት ፤ ፩
እርሱም ፡ ዘንበል ፡ አለልኝ ፡ ጩኸቴንም ፡ ሰማኝ ፡
ከጥፋት ፡ ጕድጓድ ፡ ከረግረግም ፡ ጭቃ ፡ አወጣኝ ፤ ፪
እግሮቼንም ፡ በድንጋይ ፡ ላይ ፡ አቆማቸው ፡
አረማመዴንም ፡ አጸና ።

፫ ወወደየ ፡ ውስተ ፡ አፉየ ፡ ስብሐተ ፡ ሐዲሰ ።
ስብሐቲሁ ፡ ለአምላክነ ።
ይርአዩ ፡ ብዙኃን ፡ ወይፍርሁ ።
ወይትወከሉ ፡ በእግዚአብሔር ።
፬ ብፁዕ ፡ ብእሲ ፡ ዘስመ እግዚአብሔር ፡ ትውክልቱ ።
ወዘኢነጸረ ፡ ውስተ፡ከንቱ ፡ ውስተ፡ መዓት ፡ ወሐሰት።
፭ ብዙኃ ፡ ገበርከ ፡ እግዚኦ ፡ አምላኪየ ፡ መንክረከ ።
ወአልቦ ፡ ዘይመስሎ ፡ ለኃሊናከ ።
አይዳዕኩ ፡ ወነገርኩ ፡ ወበዝኁ ፡ እምኈልቍ ።
፮ መሥዋዕተ ፡ ወቍርባነ ፡ ኢፈቀድከ ።
ሥጋከ ፡ አንጽሕ ፡ ሊተ ።
መሥዋዕተ ፡ ዘበእንተ ፡ ኃጢአት ፡ ኢሠመርከ ።
፯ ውእተ ፡ ጊዜ ፡ እቤ ፡ ነየ ፡ መጻእኩ ።
ውስተ ፡ ርእሰ ፡ መጽሐፍ ፡ ተጽሕፈ ፡ በእንቲአየ ።
፰ ከመ ፡ እንግር ፡ ፈቃደከ ፡ መከርኩ ፡ አምላኪየ ።
ወሕግከኒ ፡ በማእከለ ፡ ከርሥየ ።
፱ ዜኖኩ ፡ ጽድቀከ ፡ በማኅበር ፡ ዐቢይ ።
ወናሁ ፡ ኢከላእኩ ፡ ከናፍርየ ።
እግዚኦ ፡ ለሊከ ፡ ተአምር ፡ ጽድቅየ ።
፲ ወኢኀባእኩ ፡ ውስተ ፡ ልብየ ፡ ርትዐከ ።
ወነገርኩ ፡ አድኅኖተከ ።
ወኢሠወርኩ ፡ ሣህለከ ፡ ወምሕረተከ ፡ እማኅበር ፡ ዐቢይ ።
፲፩ አንተ ፡ እግዚኦ ፡ ኢታርኅቅ ፡ ሣህለከ ፡ እምኔየ ።
ምሕረትከ ፡ ወጽድቅከ ፡ ዘልፈ ፡ ይርከባኒ ።
፲፪ እስመ ፡ ረከበተኒ ፡ እኪት ፡ እንተ ፡ አልባቲ ፡ ኈልቍ።
ወተራከባኒ ፡ ኃጣውእየ ፡ ወስእንኩ ፡ ነጽሮ ።
ወበዝኁ ፡ እምሥእርተ ፡ ርእስየ ። ልብየኒ ፡ ኀደገኒ ።
፲፫ ሥመር ፡ እግዚኦ ፡ ከመ ፡ ታድኅነኒ ።
እግዚኦ ፡ ነጽር ፡ ውስተ ፡ ረዲአትየ ።
፲፬ ይትኀፈሩ ፡ ወይኅስሩ ፡ ኅቡረ ፡ እለ ፡ ይፈቅዱ ።
ያእትትዋ ፡ ለነፍስየ ።
፲፭ ለይግብኡ ፡ ድኅሬሆሙ ፡ ወይትኀፈሩ፡ እለ፡ ይፈቅዱ ፡ ሊተ ፡ እኩየ ።
ወይትፈደዩ ፡ በጊዜ ፡ ኃሣርሙ፡ እለ ፡ ይብሉኒ ፡ እንቋዕ ፡ እንቋዕ ።
፲፮ ለይትፈሥሑ ፡ ወይትሐሠዩ ፡ ብከ ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡
የሐሡከ ፡ እግዚኦ ።
ወይበሉ ፡ ዘልፈ ፡ ዐቢይ ፡ እግዚአብሔር ፡
እለ ፡ ይፈቅዱ ፡ አድኅኖተከ ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ።
፲፯ አንሰ ፡ ነዳይ ፡ ወምስኪን ፡ አነ ።
ወእግዚአብሔር ፡ይሔሊ ፡ ሊተ ።
ረዳኢየ፡ ወመድኅንየ፡ አንተ፡አምላኪየ፡ ወኢትጐንዲ ።

መዝሙር ፡ ፵ ።

በእንተ ፡ ሕዝቅያስ ።

፩ ብፁዕ ፡ ዘይሌቡ ፡ ላዕለ ፡ ነዳይ ፡ ወምስኪን ።
እምዕለት ፡ እኪት ፡ ያድኅኖ ፡ እግዚአብሔር ።
፪ እግዚአብሔር ፡ የዐቅቦ ፡ ወያሐይዎ ፡ ወያበፅዖ ፡ ዲበ ፡ ምድር ።
ወኢያገብኦ ፡ ውስተ ፡ እደ ፡ ጸላዒሁ ።
፫ እግዚአብሔር ፡ ይረድኦ ፡ ውስተ ፡ ዐራተ ፡ ሕማሙ ።
ወይመይጥ ፡ ሎቱ ፡ ኵሎ ፡ ምስካቤሁ ፡ እምደዌሁ ።
፬ አንሰ ፡ እቤ ፡ እግዚኦ ፡ ተሣሀለኒ ።
ወሥረይ ፡ ላቲ ፡ ለነፍስየ ፡ እስመ ፡ አበስኩ ፡ ለከ ።
፭ ጸላእትየሰ ፡ እኩየ ፡ ይቤሉ ፡ ላዕሌየ ።
ማእዜ ፡ ይመውት ፡ ወይሰዐር ፡ ስሙ ።



ለአምላካችን ፡ ምስጋና ፡ አዲስ ፡ ዝማሬን ፡ በአፌ ፡ ፫
ጨመረ ፤ ብዙዎች ፡ ያያሉ ፡ ይፈሩማል ፡
በእግዚአብሔር ፡ ይታመናሉ ።
በእግዚአብሔርም ፡ የታመነ ፡ ፬
ወደ ፡ ትዕቢተኞና ፡ ወደ ፡ ሐሰተኛ ፡ ያልተመለከተ ፡
ሰው ፡ ምስጉን ፡ ነው ።
አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ ያደረግኸው ፡ ተአምራት ፡ ብዙ ፡ ነው ፡ ፭
አሳብህንም ፡ ምንም ፡ የሚመስለው ፡ የለም ፤
ባወራም ፡ ብናገርም ፡ ከቍጥር ፡ ሁሉ ፡ በዛ ።
መሥዋዕትንና ፡ ቍርባንን ፡ አልወደድህም ፡ ፮
ሰውነቴን ፡ አንፃህልኝ ፡
የሚቃጠለውንና ፡ ስለ ፡ ኃጢአት ፡ የሚቀርበውን ፡
መሥዋዕት ፡ አልፈቀድህም ።
በዚያን ፡ ጊዜ ፡ አልሁ ፡ እነሆ ፡ መጣሁ ፡ ፯
ስለ ፡ እኔ ፡ በመጽሐፍ ፡ አርእስት ፡ ተጽፎአል ።
አምላኬ ፡ ሆይ ፡ ፈቃድህን ፡ ለማድረግ ፡ ወደድሁ ፤ ፰
ሕግህም ፡ በልቤ ፡ ውስጥ ፡ ነው ።
በታላቅ ፡ ጉባኤ ፡ ጽድቅን ፡ አወራሁ ፡ ፱
እነሆ ፡ ከንፈሮቼን ፡ አልከለከልም ፡
አቤቱ ፡ አንተ ፡ ጽድቄን ፡ ታውቃለህ ።
እውነትህንም ፡ በልቤ ፡ ውስጥ ፡ አልሰወርሁም ፡ ፲
ማዳንህንም ፡ ተናገርሁ ፤ ምሕረትህንና ፡ እውነትህን ፡
ከታላቅ ፡ ጉባኤ ፡ አልሰወርሁም ።
አቤቱ ፡ አንተ ፡ ምሕረትህን ፡ ከእኔ ፡ አታርቅ ፡ ፲፩
ቸርነትህና ፡ እውነትህ ፡ ዘወትር ፡ ይጠብቁኝ ።
ቍጥር ፡ የሌላት ፡ ክፋት ፡ አግኝታኛለችና ፡ ፲፪
ኃጢአቶቼ ፡ ያዙኝ ፡ ማየትም ፡ ተሰኖኛል ፤
ከራሴ ፡ ጠጕር ፡ ይልቅ ፡ በዙ ፡ ልቤም ፡ ከዳኝ ።
አቤቱ ፡ ታድነኝ ፡ ዘንድ ፡ ፍቀድ ፤ ፲፫
አቤቱ ፡ እኔን ፡ ለመርዳት ፡ ፍጠን ።
ነፍሴን ፡ ለማጥፋት ፡ የሚፈልጉ ፡ ይፈሩ ፡ ፲፬
በአንድነትም ፡ ይጐስቍሉ ፤
በእኔ ፡ ላይ ፡ ክፋትን ፡ ሊያደርጉ፡የሚወዱ ፡ ሁሉ ፡
ወደ ፡ ኋላቸው ፡ ይመለሱ ፡ ይጐስቍሉም ።
እሰይ ፡ እሰይ ፡ የሚሉብኝም ፡ ይፈሩ ፡ ፲፭
ውርደታቸውን ፡ ወዲያው ፡ ይቀበሉ ።
አቤቱ ፡ የሚፈልጉህ ፡ ሁሉ ፡ ፲፮
በአንተ ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ፡ ሐሤትንም ፡ ያድርጉ ፤
ሁል ፡ ጊዜ ፡ ማዳንህን ፡ የሚወዱ ፡
ዘወትር ፡ እግዚአብሔር ታላቅ ፡ ይሁን ፡ ይበሉ ።
እኔ ፡ ችግረኛና ፡ ምስኪን ፡ ነኝ ፡ ፲፯
ጌታ ፡ ግን ፡ ያስብልኛል ፤
አንተ ፡ ረዳቴና ፡ መድኃኒቴ ፡ ነህ ፤
አምላኬ ፡ ሆይ ፡ አትዘግይ ።

መዝሙር ፡ ፵ ።

ስለ ፡ ሕዝቅያስ ።

ለችግረኛና ፡ ለምስኪኑ ፡ የሚያስብ ፡ ምስጉን ፡ ነው ፤ ፩
እግዚአብሔር ፡ በክፉ ፡ ቀን ፡ ያድነዋል ።
እግዚአብሔር ፡ ይጠብቀዋል፡ ሕያውም፡ ያደርገዋል ፡ ፪
በምድር ፡ ላይም ፡ ያስመሰግነዋል ፡
በጠላቶቹም ፡ እጅ ፡ አሳልፎ ፡ አይሰጠውም ።
እግዚአብሔርም በደዌው፡አልጋ ፡ ላይ ፡ ሳለ፡ ይረዳዋል ፡ ፫
መኝታውን ፡ ሁሉ ፡ በሕመሙ ፡ ጊዜ ፡ ያነጥፍለታል ።
አቤቱ ፡ እኔንስ ፡ ማረኝ ፤ ፬
አንተን ፡ በድያለሁና ፡ ነፍሴን ፡ ፈውሳት ፡ እላለሁ ።
ጠላቶቼም ፡ በኔ ፡ ላይ ፡ ክፋትን ፡ ይናገራሉ ፡ ፭
መቼ ፡ ይሞታል ፡ ስሙስ ፡ መቼ ፡ ይጠፋል ? ይላሉ ።

፮ ይባእ ፡ ወይርአይ ፡ ዘከንቶ ፡ ይነብብ ።
ልቡ ፡ አስተጋብአ ፡ ኃጢአተ ፡ ላዕሌሁ ።
ይወፅእ ፡ አፍአ ፡ ወይትናገር ፡ ወየኀብር ፡ ላዕሌየ ።
፯ ወይትቃጸቡኒ ፡ ኵሎሙ ፡ ጸላእትየ ።
ወይመክሩ ፡ እኩየ ፡ ላዕሌየ ።
፰ ነገረ ፡ ጌጋይ ፡ አውፅኡ ፡ ላዕሌየ ።
ዘኖመሰ ፡ ኢይነቅህኑ ፡ እንከ ።
፱ ብእሲ ፡ ሰላምየ ፡ ዘኪያሁ ፡ እትአመን ።
ዘይሴሰይ ፡ እክልየ ፡ አንሥአ ፡ ሰኰናሁ ፡ ላዕሌየ ።
፲ አንተ ፡ እግዚኦ ፡ ተሣሀለኒ ፡ ወአንሥአኒ ፡ እፍድዮሙ ።
በእንተዝ ፡ አእመርኩ ፡ ከመ ፡ ሠመርከኒ ።
፲፩ ወኢተፈሥሑ ፡ ጸላእትየ ፡ ላዕሌየ ።
፲፪ ወሊተሰ ፡ በእንተ ፡ የዋሀትየ ፡ ተወከፍከኒ ።
ወአጽናዕከኒ ፡ ቅድሜከ ፡ ለዓለም ።
ይትባረክ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላከ ፡ እስራኤል ።
፲፫ ለይኩን ፡ ወእስከ ፡ ለዓለም ፡ ለይኩን ፡ ለይኩን ።

መዝሙር ፡ ፵፩ ።

በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ ከመ ፡ ያፈቅር ፡ ሀየል ፡ ኀበ ፡ አንቅዕተ ፡ ማያት ።
ከማሁ ፡ ታፈቅር ፡ ነፍስየ ፡ ኀበ ፡ እግዚአብሔር ።
፪ ጸምዓት ፡ ነፍስየ ፡ ኀበ ፡ አምላኪየ ፡ ሕያው ።
ማእዜ ፡ እበጽሕ ፡ ወእሬኢ ፡ ገጾ ፡ ለአምላኪየ ።
፫ ሲሳየ ፡ ኮነኒ ፡ አንብዕየ ፡ መዓልተ ፡ ወሌሊተ ።
እስመ፡ይብሉኒ፡ኵሎ፡አሚረ፡አይቴ፡ውእቱ፡ አምላክከ ።
፬ ዘንተ ፡ ተዘኪርየ ፡ ተክዕወት ፡ ነፍስየ ፡ በላዕሌየ ።
እስመ ፡ እበውዕ ፡ ውስተ ፡ መካን ፡ ማኅደረ ፡ ስብሐት
ቤተ ፡ እግዚአብሔር ።
በቃለ ፡ አሚን ፡ ወበትፍሥሕት ፡ ደምፀ ፡ እለ ፡ ይገብሩ ፡ በዓለ ።
፭ ለምንት ፡ ትቴክዚ ፡ ነፍስየ ፡ ወለምንት ፡ ተሀውክኒ ።
እመኒ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ከመ ፡ እገኒ ፡ ሎቱ ።
መድኃኔ ፡ ገጽየ ፡ አምላኪየ ።
፮ ተሀውከት ፡ ነፍስየ ፡ በላዕሌየ ።
በእንተዝ ፡ እዜከረከ ፡ እግዚኦ ።
በምድረ ፡ ዮርዳኖስ ፡ በአርሞንኤም ፡ በደብር ፡ ንዑስ።
፯ ቀላይ ፡ ለቀላይ ፡ ትጼውዕ ፡ በቃለ ፡ አስራቢከ ።
ኵሉ ፡ ማዕበልከ ፡ ወሞገድከ ፡ እንተ ፡ ላዕሌየ ፡ ኀለፈ ።
፰ መዓልተ ፡ ይኤዝዝ ፡ እግዚአብሔር፡ ሣህሎ፡ ወሌሊተ፡ ይነግር ።
እምኀቤየ ፡ ብፅዕተ ፡ ሕይወትየ ፡ ለእግዚአብሔር ።
፱ እብሎ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አምላኪየ ፡ አንተ ፡ ለምንት ፡ ትረስዐኒ ።
ለምንት ፡ ተኀድገኒ ፡ ወለምንት ፡ ትኩዝየ ፡ አንሶሱ ።
ሶበ ፡ ያመነድቡኒ ፡ ፀርየ ። ወያጸንጽውኒ ፡ አዕዕምትየ ።
ወይጼእሉኒ ፡ ኵሎሙ ፡ ጸላእትየ ።
፲ እስመ፡ይብሉኒ፡ኵሎ፡አሚረ፡አይቴ፡ውእቱ፡ አምላክከ ።
፲፩ ለምንት ፡ ትቴክዚ ፡ ነፍስየ ፡ ወለምንት ፡ ተሀውክኒ ።
እመኒ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ከመ ፡ እገኒ ፡ ሎቱ ።
መድኅኔ ፡ ገጽየ ፡ አምላኪየ ።

መዝሙር ፡ ፵፪ ።
በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ ፍታሕ ፡ ሊተ ፡ እግዚኦ ፡ ወተበቀል ፡ በቀልየ ።
እምሕዝብ ፡ ውፁኣን ፡ እምጽድቅ ።
ምብእሲ ፡ ዐማፂ ፡ ወጽልሕው ፡ ባልሐኒ ።



እኔን ለማየት፡ የተገባው ፡ ቢሆን ፡ ከንቱን ፡ ይናገራል ፡ ፮
ልቡ ፡ ኃጢአትን ፡ ይሰበስባል ፤
ወደ ፡ ሜዳም ፡ ይወጣል ፡ ይናገራልም ።
በላዬ፡ በመተባበር፡ ጠላቶቼ፡ሁሉ ፡ ይንሾካሾኩብኛል ፡ ፯
በእኔ ፡ ላይም ፡ ክፋትን ፡ ያስባሉ ።
ክፉ ፡ ነገር ፡ መጣበት ፡ ተኝቶአል ፡ ፰
ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አይነሣም ፡ ይላሉ ።
ደግሞ ፡ የሰላሜ ፡ ሰው ፡ የታመንሁበት ፡ ፱
እንጀራዬን ፡ የበላ ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ተረከዙን ፡ አነሣ ።
አንተ ፡ ግን ፡ አቤቱ ፡ ማረኝ ፡ ፲
እመልስላቸውም ፡ ዘንድ ፡ አስነሣኝ ።
ጠላቴ ፡ እልል ፡ ይልብኝ ፡ ዘንድ ፡ አልፈልግምና ፡ ፲፩
ስለዚህ ፡ እንደ ፡ ወደድኸኝ ፡ አወቅሁ ።
እኔን ፡ ግን ፡ ስለ ፡ ቅንነቴ ፡ ተቀበልኸኝ ፡ ፲፪
በፊትህም ፡ ለዘለዓለም ፡ ታኖረኛለህ ።
ከዘላለም ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ድረስ ፡ ፲፫
የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይባረክ ።
አሜን ፡ አሜን ።

መዝሙር ፡ ፵፩ ።

ስለ ትሩፋን ።

ዋሊያ ፡ ወደ ፡ ውኃ ፡ ምንጭ ፡ እንደሚናፍቅ ፡ ፩
አቤቱ ፡ እንዲሁ ፡ ነፍሴ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ትናፍቃለች ።
ነፍሴ ፡ ሕያው ፡ አምላክን ፡ ተጠማች ፤ ፪
መቼ ፡ እደርሳለሁ ? የአምላክንስ፡ ፊት፡መቼ ፡ አያለሁ ?
ዘወትር ፡ አምላክህ ፡ ወዴት ፡ ነው ? ሲሉኝ ፡ ፫
እንባዬ ፡ በቀንና ፡ በሌሊት ፡ ምግብ ፡ ሆነኝ ።
ይህን ፡ ባሰብሁ ፡ ጊዜ ፡ ነፍሴ ፡ በእኔ ፡ ውስጥ፡ፈሰሰች ፡ ፬
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ የምስጋና ፡ አዳራሽ ፡
እገባ ፡ ነበርና ፤
በዓል ፡ የሚያደርጉ ፡ ሰዎች፡ የደስታና፡የምስጋና፡ቃል፡
አሰሙ ።
ነፍሴ ፡ ሆይ፡ ለምን ?ታዝኛለሽ? ለምንስ፡ታውኪኛለሽ፡ ፭
የፊቴን ፡ መድኃኒት ፡ አምላኬን ፡ አመሰግነው ፡
ዘንድ ፡ በእግዚአብሔር ታመኚ ።
አምላኬ ፡ ሆይ ፡ ነፍሴ ፡ በእኔ ፡ ውስጥ ፡ ታወከች ፡ ፮
ስለዚህ ፡ በዮርዳኖስ ፡ ምድር ፡ በአርሞንኤምም ፡
በታናሹ ፡ ተራራ ፡ አስብሃለሁ ።
በፏፏቴህ ፡ ድምፅ ፡ ቀላይ ፡ ቀላይን፡ ትጠራታለች ፡ ፯
ማዕበልህና ፡ ሞገድህ ፡ ሁሉ ፡ በላዬ ፡ አለፈ ።
እግዚአብሔር ፡ በቀን ፡ ቸርነቱን ፡ ያዝዛል ፡ ፰
በሌሊትም ፡ ዝማሬው ፡ በእኔ ፡ ዘንድ፡ይሆናል ፤
የእኔ ፡ ስእለት ፡ ለሕይወቴ ፡ አምላክ ፡ ነው ።
እግዚአብሔርን አንተ፡ መጠጊያዬ፡ ነህ፡ ለምን፡ ረሳኸኝ ? ፱
ጠላቶቼ ፡ ሲያስጨንቁኝ ፡ ለምን፡ አዝኜ፡ እመላለሳለሁ ?
እለዋለሁ ።
ጠላቶቼ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ አምላክህ ፡ ወዴት ፡ ነው ?
ባሉኝ ፡ ጊዜ ፡ ፲
አጥንቶቼን ፡ እየቀለጣጠሙ ፡ ሰደቡኝ ።
ነፍሴ፡ሆይ፡ለምን፡ ታዝኛለሽ?ለምንስ ፡ታውኪኛለሽ ? ፲፩
የፊቴን ፡ መድኃኒት ፡ አምላኬን ፡ አመሰግነው ፡
ዘንድ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ታመኚ ።

መዝሙር ፡ ፵፪ ።
ስለ ትሩፋን ።

አቤቱ ፡ ፍረድልኝ ፡ ፩
ከዕውነት ፡ የራቁ ፡ ሕዝብም ፡ ጋር ፡ ስለኔ ፡ ተከራከር ፡
ከሸንጋይና ፡ ከግፈኛ ፡ ሰው ፡ አድነኝ ።

፪ እስመ ፡ አንተ ፡ አምላኪየ ፡ ወኀይልየ ።
ለምንት ፡ ተገድፈኒ ፡ ወለምንት ፡ ትከዝየ ፡ አንሶሱ ።
ሶበ ፡ ያመንድቡኒ ፡ ፀርየ ።
፫ ፈኑ ፡ ብርሃነከ ፡ ወጽድቀከ ።
እማንቱ ፡ ይምርሓኒ ፡ ወይሰዳኒ ፡ ደብረ ፡ መቅደስከ ።
ወውስተ ፡ አብያቲከ ፡ እግዚኦ ።
፬ እበውእ ፡ ኀበ ፡ ምሥዋዒሁ ፡ ለእግዚአብሔር ።
ኀበ ፡ አምላኪየ ፡ ዘአስተፌሥሓ ፡ ለውርዙትየ ።
እገኒ ፡ ለከ ፡ አምላኪየ ፡ በመሰንቆ ።
፭ ለምንት ፡ ትቴክዚ ፡ ነፍስየ ፡ ወለምንት ፡ ተሀውከኒ ።
እመኒ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ከመ ፡ እገኒ ፡ ሎቱ ።
መድኀኔ ፡ ገጽየ ፡ አምላኪየ ።

መዝሙር ፡ ፵፫ ።

በእንተ ፡ መቃብያን ።

፩ እግዚኦ ፡ ሰማዕነ ፡ በእዘኒነ ።
ወአበዊነሂ ፡ ዜነዉነ ።
ግብረ ፡ ዘገበርከ ፡ በመዋዕሊሆሙ ፡ በመዋዕለ፡ትካት።
፪ እዴከ ፡ ሠረወቶሙ ፡ ለፀር ፡ ወተከልከ ፡ ኪያሆሙ ።
ሣቀይኮሙ ፡ ለአሕዛብ ፡ ወሰደድኮሙ ።
ዘአኮ ፡ በኲናቶሙ ፡ ወረስዋ ፡ ለምድር ።
ወመዝራዕቶሙኒ ፡ ኢያድኀኖሙ ።
፫ ዘእንበለ ፡ የማንከ ፡ ወመዝራዕትከ ፡ ወብርሃነ ፡ ገጽከ።
እስመ ፡ ተሣሀልኮሙ ።
፬ አንተ ፡ ውእቱ ፡ ንጉሥየ ፡ ወአምላኪየ ።
ዘአዘዝከ ፡ መድኃኒቶ ፡ ለያዕቆብ ።
፭ ብከ ፡ ንወግዖሙ ፡ ለኵሎሙ ፡ ፀርነ ።
ወበስምከ ፡ ናኀስሮሙ ፡ ለእለ ፡ ቆሙ ፡ ላዕሌነ ።
፮ ዘአኮ ፡ በቀስትየ ፡ እትአመን ።
ወኲናትየኒ ፡ ኢያድኀነኒ ።
፯ ወአድኀንከነ ፡ እምእለ ፡ ሮዱነ ።
ወአስተኀፈርኮሙ ፡ ለኵሎሙ ፡ ጸላእትነ ።
፰ በእግዚአብሔር ፡ ንከብር ፡ ኵሎ ፡ አሚረ ።
ወለስምከ ፡ ንገኒ ፡ ለዓለም ።
፱ ይእዜሰ ፡ ገደፍከነ ፡ ወአስተኀፈርከነ ።
ወኢትወፅእ ፡ አምላክነ ፡ ምስለ ፡ ኀይልነ ።
፲ ወአግባእከነ ፡ ድኅሬነ ፡ ኀበ ፡ ፀርነ ።
ወተማሰጡነ ፡ ጸላእትነ ።
፲፩ ወወሀብከነ ፡ ይብልዑነ ፡ ከመ ፡ አባግዕ ።
ወዘረውከነ ፡ ውስተ ፡ አሕዛብ ።
፲፪ ወመጦከ ፡ ሕዝበከ ፡ ዘእንበለ ፡ ሤጥ ።
ወአልቦ ፡ ብዝኀ ፡ ለይባቤነ ።
፲፫ ወረሰይከነ ፡ ጽዕለተ ፡ ለጎርነ ።
ሠሐቀ ፡ ወሥላቀ ፡ ለአድያሚነ ።
፲፬ ወረሰይከነ ፡ አምሳለ ፡ ለአሕዛብ ።
ወሑስተ ፡ ርእስ ፡ ለሕዝብ ።
፲፭ ኵሎ ፡ አሚረ ፡ ቅድሜየ ፡ ውእቱ ፡ ኀፍረትየ ።
ወከደነኒ ፡ ኀፍረት ፡ ገጽየ ።
፲፮ እምቃለ ፡ ዘይጸዕል ፡ ወይዘረኪ ።
እምገጸ ፡ ፀራዊ ፡ ዘይረውድ ።
፲፯ ዝንቱ ፡ ኵሉ ፡ በጽሐ ፡ ላዕሌነ ፡ ወኢረሳዕናከ ።
ወኢዐመፅነ ፡ ኪዳነከ ።
፲፰ ወኢገብአ ፡ ድኅሬሁ ፡ ልብነ ።
ወኢተግሕሠ ፡ አሠርነ ፡ እምፍኖትከ ።
፲፱ እስመ ፡ አሕመምከነ ፡ በብሔር ፡ እኩይ ፤ ወድፈነነ ፡ ጽላሎተ ፡ ሞት ።
፳ ሰበሁ ፡ ረሳዕነ ፡ ስመ ፡ ለአምላክነ ።
ወሰበሁ ፡ አንሣእነ ፡ እደዊነ ፡ ኀበ ፡ አምላክ ፡ ነኪር ።



አንተ ፡ አምላኬ ፡ ኃይሌም ፡ ለምን ፡ ትተወኛለህ ? ፪
ጠላቶቼ ፡ ሲያስጨንቁኝ ፡ ለምን ፡ አዝኜ ፡ እመላለሳለሁ ?
ብርሃንህንና ፡ እውነትህን ፡ ላክ ፤ ፫
እነርሱ ፡ ይምሩኝ ፡
ወደ ፡ ቅድስናህ ፡ ተራራና ፡ ወደ ፡ ማደሪያህ ፡ ይውሰዱኝ ።
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡ ፬
ጕልማስነቴንም ፡ ደስ ፡ ወዳሰኛት ፡
ወደ ፡ አምላኬ ፡ እገባለሁ ፤
አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ በበገና ፡ አመሰግንሃለሁ ።
ነፍሴ ፡ ሆይ ፡ ለምን ፡ ታዝኛለሽ ፡ ለምንስ ፡ ታውኪኛለሽ ፤ ፭
የፊቴን ፡ መድኃኒት ፡ አምላኬን ፡ አመሰግነው ፡ ዘንድ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ታመኚ ።

መዝሙር ፡ ፵፫ ።

ስለ መቃብያን ።

አቤቱ ፡ በጆሮአችን ፡ ሰማን ፤
አባቶቻችንም ፡ በዘመናቸው ፡ በቀድሞ ፡ ዘመን ፡
የሠራኸውን ፡ ሥራ ፡ ነገሩን ።
እጅህ ፡ አሕዛብን ፡ አጠፋች ፡ ወገኖችህንም ፡ ተከልህ ፤ ፪
አሕዛብን ፡ ጣቀይሃቸው ፡ አሳደድካቸውም ።
በሰይፋቸው ፡ ምድርን ፡ አልወረሱም ፤ ፫
ክንዳቸውም ፡ አላዳናቸውም ፡ ቀኝህና ፡ ክንድህ ፤
የፊትህም ፡ ብርሃን ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ ወደሃቸዋልና ።
አምላኬና ፡ ንጉሤ ፡ አንተ ፡ ነህ ፤ ፬
ለያዕቆብ ፡ መድኃኒትን ፡ እዘዝ ።
በአንተ ፡ ጠላቶቻችንን ፡ እንወጋቸዋለን ፤ ፭
በስምህም ፡ በላያችን ፡ የቆሙትን ፡ እናዋርዳቸዋለን ።

በቀስቴ ፡ የምታመን ፡ አይደለሁምና ፤ ፮
ሰይፌም ፡ አያድነኝምና ።
አንተ ፡ ግን ፡ ከጠላቶቻችን ፡ አዳንኸን ፤ ፯
የሚጠሉንንም ፡ አሳፈርሃቸው ።
ሁል ፡ ጊዜ ፡ በእግዚአብሔር ፡ እንከብራለን ፤ ፰
ስምህንም ፡ ለዘላለም ፡ እናመሰግናለን ።
አሁን ፡ ግን ፡ ጣልኸን ፡ አሳፈርኸንም ፤ ፱
ከሠራዊታችን ፡ ጋር ፡ አልወጣህምና ።
ከጠላቶቻችን ፡ ፊት ፡ ወደ ፡ ኋላችን ፡ መለስኸን ፤ ፲
የሚጠሉንም ፡ ተነጣጠቁን ።
እንደ ፡ በጎች ፡ ሊበሉን ፡ አሳልፈህ ፡ ሰጠኸን ፤ ፲፩
ወደ ፡ አሕዛብም ፡ በተንኸን ።
ሕዝብህን ፡ ያለ ፡ ዋጋ ፡ ሰጠህ ፤ ፲፪
ስለርሳቸውም ፡ ለውጥ ፡ አልተቀበልህም ፤
ለምስጋናችን ፡ ብዛት ፡ የለውም ።
ለጎረቤቶቻችን ፡ ስድብ ፤ ፲፫
በዙሪያችንም ፡ ላሉ ፡ መሣቂያና ፡ መዘበቻ ፡ አደረግኸን ።
በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ ምሳሌ ፤ በሕዝብም ፡ ዘንድ ፡ ፲፬
የራስ ፡ መነቅነቂያ ፡ አደረግኸን ።
ጕስቍልናዬ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ በፊቴ ፡ ነው ፤ ፲፭
የፊቴም ፡ እፍረት ፡ ሸፈነኝ ።
ከሚሳደብና ፡ ከሚላገድ ፡ ቃል ፤ ፲፮
ከጠላትና ፡ ከቂመኛም ፡ ፊት ፡ የተነሣ ።
ይህ ፡ ሁሉ ፡ በእኛ ፡ ላይ ፡ ደረሰ ፤ እኛ ፡ ግን ፡ አልረሳንህም ፤ ፲፯
ኪዳንህንም ፡ አልወነጀልንም ።
ልባችን ፡ ወደ ፡ ኋላው ፡ አልተመለሰም ፤ ፲፰
ፍለጋችንም ፡ ከመንገድህ ፡ ፈቀቅ ፡ አላለም ።
በክፉ ፡ ስፍራ ፡ አዋርደኸናልና ፤ በሞት ፡ ጥላም ፡ ሰውረኸናልና ። ፲፱
የአምላካችንን ፡ ስም ፡ ረስተንስ ፡ ቢሆን ፤ ፳
እጃችንንም ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ አምላክ ፡ አንሥተንስ ፡ ቢሆን ፤

፳፩ አኮኑ ፡ እግዚአብሔር ፡ እምተኀሠሠ ፡ ለዝንቱ ።
እስመ ፡ ውእቱ ፡ የአምር ፡ ኅቡአተ ፡ ልብነ ።
፳፪ እስመ ፡ በእንቲአሁ ፡ ይቀትሉነ ፡ ኵሎ ፡ አሚረ ።
ወኮነ ፡ ከመ ፡ አባግዕ ፡ ዘይጠብሑ ።
፳፫ ንቃህ ፡ እግዚኦ ፡ ለምንት ፡ ትነውም ።
ተንሥእ ፡ ወኢትግድፈነ ፡ ለዝሉፉ ።
፳፬ ወለምንት ፡ ትመይጥ ፡ ገጸከ ፡ እምኔነ ።
ወትረስዐነ ፡ ሕማመነ ፡ ወተጽናሰነ ።
፳፭ እስመ ፡ ኅሠረት ፡ ውስተ ፡ ምድር ፡ ነፍስነ ።
ወጠግዐት ፡ በምድር ፡ ከርሥነ ።
፳፮ ተንሥእ ፡ እግዚኦ ፡ ርድአነ ።
ወአድኅነነ ፡ በእንተ ፡ ስምከ ።

መዝሙር ፡ ፵፬ ።

ትንቢት ፡ በእንተ ፡ ክርስቶስ ፡ ወማርያም ።

፩ ጐሥዐ ፡ ልብየ ፡ ቃለ ፡ ሠናየ ።
ወአነ ፡ አየድዕ ፡ ግብርየ ፡ ለንጉሥ ።
ከመ ፡ ቀለመ፡ጸሐፊ፡ ዘጠበጠበ፡ ይጽሕፍ፡ ልሳንየ ።
፪ ይሤኒ ፡ ላሕዩ ፡ እምውሉደ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ።
ተክዕወ ፡ ሞገስ ፡ እምከናፍሪከ ።
በእንተዝ ፡ ባረከከ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለዓለም ።
፫ ቅንት ፡ ሰይፈከ ፡ ኀያል ፡ ውስተ ፡ ሐቌከ ።
በስንከ ፡ ወበላሕይከ ።
አርትዕ ፡ ተሠራሕ ፡ ወንግሥ ።
፬ በእንተ ፡ ጽድቅ ፡ ወርትዕ ፡ ወየዋሀት ።
ወይመርሐከ ፡ ስብሐተ ፡ የማንከ ።

፭ አሕጻከ ፡ ስሑል ፡ ኀያል ።
አሕዛብ ፡ ይወድቁ ፡ ታሕቴከ ።
ውስተ ፡ ልበሙ ፡ ለጸላእተ ፡ ንጉሥ ።
፮ መንበርከ ፡ እግዚኦ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ።
በትረ ፡ ጽድቅ ፡ ወበትረ ፡ መንግሥትከ ።
፯ አፍቀርከ ፡ ጽድቀ ፡ ወዐመፃ ፡ ጸላእከ ።
በእንተዝ ፡ ቀብዐከ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክከ ።
ቅብዐ ፡ ትፍሥሕት ፡ እምእለ ፡ ከማከ ።
፰ ከርቤ ፡ ወቀንዓት ፡ ወሰሊሖት ፡ እምነ ፡ አልባሲከ ።
እምክቡዳነ ፡ አቅርንት ፡ ዘእምኔሆሙ ፡ አስተፌሥሑከ
፱ አዋልደ ፡ ንግሥት ፡ ለክብርከ ።
ወትቀውም ፡ ንግሥት ፡ በየማንከ ።
በአልባሰ ፡ ወርቅ ፡ ዑጽፍት ፡ ወኊብርት ።
፲ ስምዒ ፡ ወለትየ ፡ ወርእዪ ፡ ወአጽምዒ ፡ እዝነኪ ።
ርስዒ ፡ ሕዝበኪ ፡ ወቤተ ፡ አቡኪ ።
፲፩ እስመ ፡ ፈተወ ፡ ንጉሥ ፡ ሥነኪ ።
እስመ ፡ ውእቱ ፡ እግዚእኪ ።
፲፪ ወይሰግዱ ፡ ሎቱ ፡ አዋልደ ፡ ጢሮስ ፡ በአምኃ ።
ወለገጽኪ ፡ ይትመሐለሉ ፡ ኵሎሙ ፡ አሕዛብ ፡ ብዑላነ ፡ ምድር ።
፲፫ ኵሉ ፡ ክብራ ፡ ለወለተ ፡ ንጉሠ ፡ ሐሴቦን ።
በዘአዝፋረ ፡ ወርቅ ፡ ዑጽፍት ፡ ወኊብርት ።
፲፬ ወይወስዱ ፡ ለንጉሥ ፡ ደናግለ ፡ ድኅሬሃ ።
ወቢጻሂ ፡ ይወስዱ ፡ ለከ ።
፲፭ ወይወስድዎን ፡ በትፍሥሕት ፡ ወበሐሤት ።
ወያበውእዎን ፡ ውስተ ፡ ጽርሐ ፡ ንጉሥ ።
፲፮ ህየንተ ፡ አበውኪ ፡ ተወልዱ ፡ ለኪ ፡ ደቂቅ ።
ወትሠይሚዮሙ ፡ መላእክተ ፡ ለኵሉ ፡ ምድር ።
፲፯ ወይዘክሩ ፡ ስመኪ ፡ በኵሉ ፡ ትውልደ ፡ ትውልድ ።
በእንተዝ ፡ ይገንዩ ፡ ለከ ፡ አሕዛብ ፡ እግዚኦ ።
ለዓለም ፡ ወለዓለም ፡ ዓለም ።



እግዚአብሔር ፡ ይህን ፡ አይመረምርም ፡ ነበርን ? ፳፩
እርሱ ፡ ልብ ፡ የሰወረውን ፡ ያውቃልና ።
ስለ ፡ አንተ ፡ ሁል ፡ ጊዜም ፡ ተገድለናል ፡ ፳፪
እንደሚታረዱም ፡ በጎች ፡ ሆነናል ።
አቤቱ ፡ ንቃ ፡ ለምንስ ፡ ትተኛለህ ? ፳፫
ተነሥ ፡ ለዘወትርም ፡ አትጣለን ።
ለምንስ ፡ ፊትህን ፡ ትሰውራለህ ? ፳፬
መከራችንንና ፡ ችግራችንስ ፡ ለምን ፡ ትረሳለህ ?
ነፍሳችን ፡ በመሬት ፡ ላይ ፡ ተጐሳቍላለችና ፡ ፳፭
አንጀታችንም ፡ በምድር ፡ ተጣብቃለችና ።
አቤቱ ፡ ተነሥና ፡ እርዳን ፡ ፳፮
ስለ ፡ ስምህም ፡ ታደገን።

መዝሙር ፡ ፵፬ ።

ስለክርስቶስና ፡ ስለእመቤታችን ።

ልቤ ፡ መልካም ፡ ነገርን ፡ አፈለቀ ። ፩
እኔ ፡ ሥራዬን ፡ ለንጉሥ ፡ እነግራለሁ ፡
አንደበቴ ፡ እንደ ፡ ፈጣን ፡ ጸሓፊ ፡ ብዕር ፡ ነው ።
ውበትህ ፡ ከሰው ፡ ልጆች ፡ ይልቅ ፡ ያምራል ፡ ፪
ሞገስ ፡ በከንፈሮችህ ፡ ፈሰሰ ፡
ስለዚህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ ባረከህ ።
ኃያል ፡ ሆይ ፡ በቍንጅናህና ፡ በውበትህ ፡ ፫
ሰይፍህን ፡ በወገብህ ፡ ታጠቅ ።
ስለ ፡ ቅንነትና፡ ስለ ፡ የዋህነት ፡ ስለ ፡ ጽድቅም ፡ ፬
አቅና ፡ ተከናወን ፡ ንገሥም ፤
ቀኝህም ፡ በክብር ፡ ይመራሃል ።

ኃያል ፡ ሆይ ፡ ፍላጻዎችህ ፡ የተሳሉ ፡ ናቸው ፡ ፭
እነርሱም ፡ በንጉሥ ፡ ጠላቶች ፡ ልብ ፡ ውስጥ ፡ ይገባሉ ፡
አሕዛብም ፡ በበታችህ ፡ ይወድቃሉ ።
አምላክ ፡ ሆይ ፡ ዙፋንህ ፡ ለዘላለም ፡ ነው ፡ ፮
የመንግሥትህ ፡ በትር ፡ የቅንነት ፡ በትር ፡ ነው ።
ጽድቅን ፡ ወደድህ ፡ ዓመፃንም ፡ ጠላህ ፡ ፯
ስለዚህ ፡ ከባልንጀሮችህ ፡ ይልቅ ፡ እግዚአብሔር ፡
አምላክህ ፡ የደስታ ፡ ዘይትን ፡ ቀባህ ።
በልብሶችህ ፡ ሁሉ ፡ ከርቤና ፡ሽቱ ፡ ዝባድም ፡ አሉ ፡ ፰
ከዝሆን፡ ጥርሶች፡ አዳራሽ ፡ በዝማሬ ፡ ደስ ፡ ያሰኙሃል ።
የንጉሦች ፡ ሴት ፡ ልጆች ፡ ለክብርህ ፡ ናቸው ፡ ፱
በወርቅ ፡ ልብስ ፡ ተጐናጽፋና ፡ ተሸፋፍና ፡
ንግሥቲቱ ፡ በቀኝህ ፡ ትቆማለች ።
ልጄ ፡ ሆይ ፡ ስሚ ፡ እዪ ፡ ጆሮሽንም ፡ አዘንብዪ ፡ ፲
ወገንሽን ፡ ያባትሽንም ፡ ቤት ፡ እርሺ ።
ንጉሥ ፡ ውበትሽን ፡ ወዶአልና ፡ ፲፩
እርሱ ፡ ጌታሽ ፡ ነውና ።
የጢሮስ ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ እጅ ፡ መንሻን፡ ይዘው፡ ይሰግዱለታል ። ፲፪
የምድር፡ባለጠጎች፡ አሕዛብ፡ በፊትሽ፡ ይማለላሉ ። ፲፫
ለሐሴቦን ፡ ንጉሥ ፡ ልጅ ፡ ሁሉ ፡ ክብርዋ ፡ ነው ፡
ልብስዋ ፡ የወርቅ ፡ መጐናጸፊያ ፡ ነው ።
በኋላዋ ፡ ደናግሉን ፡ ለንጉሥ ፡ ይወስዷሉ ፡ ፲፬
ባልንጀሮችዋንም ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ያቀርባሉ ።
በደስታና ፡ በሐሤት ፡ ይወስዱአቸዋል ፡ ፲፭
ወደ ፡ ንጉሥ ፡ እልፍኝም ፡ ያስገቡአቸዋል ።
በአባቶችሽ ፡ ፋንታ ፡ ልጆች ፡ ተወለዱልሽ ፡ ፲፮
በምድርም፡ሁሉ፡ገዥዎች፡ አድርገሽ፡ትሾሚያቸዋለሽ ።
ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ሁሉ ፡ ስምሽን ፡ ያሳስባሉ ፡ ፲፯
ስለዚህ ፡ ለዓለምና ፡ ለዘላለም ፡
አሕዛብ ፡ ይገዙልሃል ።

መዝሙር ፡ ፵፭ ።

በእንተ ፡ አካዘ ፡ ወሕዝቅያስ ።

፩ እግዚአብሔር ፡ ኃይልነ ፡ ወፀወንነ ።
ወረዳኢነ ፡ ውእቱ ፡ ለምንዳቤነ ፡ ዘረከበነ ፡ ፈድፋደ ።
፪ በእንተዝ ፡ ኢንፈርህ ፡ ለእመ ፡ አድለቅለቀት ፡ ምድር።
ወለእመኒ ፡ ፈለሱ ፡ አድባር ፡ ውስተ ፡ ልበ ፡ ባሕር ።
፫ ደምፁ ፡ ወተሐምጉ ፡ ማያቲሆሙ ።
ወአድለቅለቁ ፡ አድባር ፡ እምኃይሉ ።
፬ ፈለግ ፡ ዘይውኅዝ ፡ ያስተፌሥሖ ፡ ሀገረ ፡ እግዚአብሔር ።
ቀደሰ ፡ ማኅደሮ ፡ ልዑል ።
፭ እግዚአብሔር ፡ ውስተ ፡ ማእከላ ፡ ኢትትሀወክ ።
ወይረድኣ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፍጽመ ።
፮ ደንገፁ ፡ አሕዛብ ፡ ወተመይጡ ፡ ነገሥት ።
ወወሀበ ፡ ቃሎ ፡ ልዑል ፡ ወአድለቅለቀት ፡ ምድር ።
፯ እግዚአ ፡ ኀያላን ፡ ምስሌነ ።
ወምስካይነ ፡ አምላኩ ፡ ለያዕቆብ ።
፰ ንዑ ፡ ትርአዩ ፡ ግብሮ ፡ ለእግዚአብሔር ።
ዘገብረ ፡ መንክረ ፡ በዲበ ፡ ምድር ።
፱ ይሰዕር ፡ ጸብአ ፡ እምአጽናፈ ፡ ምድር ።
ይሰብር ፡ ቀስተ ፡ ወይቀጠቅጥ ፡ ወልታ ።
ወያውዒ ፡ በእሳት ፡ ንዋየ ፡ ሐቅል ።
፲ አስተርክቡ ፡ ወአእምሩ ፡ ከመ ፡ አነ ፡ ውእቱ ፡ እግዚአብሔር ።
ተለዐልኩ ፡ እምአሕዛብ ፡ ወተለዐልኩ ፡ እምድር ።
፲፩ እግዚአ ፡ ኀያላን ፡ ምስሌነ ።
ወምስካይነ ፡ አምላኩ ፡ ለያዕቆብ ።

መዝሙር ፡ ፵፮ ።

በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ ኵልክሙ ፡ አሕዛብ ፡ ጥፍሑ ፡ እደዊክሙ ።
ወየብቡ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በቃለ ፡ ትፍሥሕት ።
፪ እስመ ፡ ልዑል ፡ ወግሩም ፡ እግዚአብሔር ።
ወንጉሥ ፡ ዐቢይ ፡ ውእቱ ፡ ዲበ ፡ ኵሉ ፡ ምድር ።
፫ አግረረ ፡ ለነ ፡ አሕዛበ ፡ ወሕዝበ ፡ ታሕተ ፡ እገሪነ ።
ወኀረየነ ፡ ሎቱ ፡ ለርስቱ ።
፬ ሥኖ ፡ ለያዕቆብ ፡ ዘአፍቀረ ።
፭ ዐርገ ፡ እግዚአብሔር ፡ በይባቤ ።
ወእግዚእነ ፡ በቃለ ፡ ቀርን ።
፮ ዘምሩ ፡ ለአምላክነ ፡ ዘምሩ ።
ዘምሩ ፡ ለንጉሥነ ፡ ዘምሩ ።
፯ እስመ ፡ ንጉሥ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለኵሉ ፡ ምድር ።
፰ ዘምሩ ፡ ልብወ ፡ ነግሠ ፡ እግዚአብሔር ፡ ላዕለ ፡ ኵሉ ፡ አሕዛብ ።
እግዚአብሔርሰ ፡ ይነብር ፡ ዲበ ፡ መንበሩ ፡ ቅዱስ ።
መላእክተ ፡ አሕዛብ ፡ ተጋብኡ ፡ ምስለ ፡ አምላከ ፡ አብርሃም ።
፱ እስመ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ጽኑዓነ ፡ ምድር ፡ ፈድፋደ ፡ ተለዐሉ ።

መዝሙር ፡ ፵፯ ።

በእንተ ፡ ሕዝቅያስ ።

፩ ዐቢይ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወብዙኅ ፡ አኰቴቱ ።
በሀገረ ፡ አምላክነ ፡ በደብረ ፡ መቅደሱ ።
ዘይኤዝዝ ፡ ትፍሥሕተ ፡ ለኵሉ ፡ ምድር ።



መዝሙር ፡ ፵፮ ።

ስለ ፡ አካዝና ፡ ስለ ፡ ሕዝቅያስ ።

እግዚአብሔር ፡ መጠጊያችንና ፡ ኃይላችን ፡ ነው ፡ ፩
ባገኘን ፡ በታላቅ ፡ መከራም ፡ ጊዜ ፡ ረዳታችን ፡ ነው ።
ስለዚህ ፡ ምድር ፡ ብትነዋወጥ ፡ ፪
ተራሮችም ፡ ወደባሕር ፡ ጥልቀት ፡ ቢወሰዱ ፡ አንፈራም
ውኆቻቸው ፡ ጮኹ ፡ ተናወጡም ፡ ፫
ተራሮችም ፡ ከኃይሉ ፡ የተነሣ ፡ ተናወጡ ።
የወንዝ ፡ ፈሳሾች ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ከተማ ፡ ደስ ፡ ያሰኛሉ ፡ ፬
ልዑል ፡ ማደሪያውን ፡ ቀደሰ ።
እግዚአብሔር ፡ በመካከሏ ፡ ነው ፡ አትናወጥም ፡ ፭
እግዚአብሔርም ፡ ፈጥኖ ፡ ይረዳታል ።
አሕዛብ ፡ ተናወጡ ፡ መንግሥታትም ፡ ተመለሱ ፡ ፮
እርሱ ፡ ቃሉን ፡ ሰጠ ፡ ምድርም ፡ ተንቀጠቀጠች ።
የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ነው ፡ ፯
የያዕቆብም ፡ አምላክ ፡ መጠጊያችን ፡ ነው ።
የእግዚአብሔርን ፡ ሥራ ፡ ፰
በምድር ፡ ያደረገውንም ፡ ተአምራት ፡ እንድታዩ ፡ ኑ ።
እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ ጦርነትን ፡ ይሽራል ፡ ፱
ቀስትን ፡ ይሰብራል ፡ ጦርንም ፡ ይቆራርጣል ፡
በእሳትም ፡ ጋሻን ፡ ያቃጥላል ።
ዕረፉ ፡ እኔም ፡ አምላክ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ እወቁ ፡ ፲
በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ እላለሁ ፡
በምድርም ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ እላለሁ ።
የሠራዊት ፡ ጌታ ፡ ከእኛ ፡ ጋር ፡ ነው ፡ ፲፩
የያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ መጠጊያችን ፡ ነው ።

መዝሙር ፡ ፵፯ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

አሕዛብ ፡ ሁላችሁ ፡ በእጆቻችሁ ፡ አጨብጭቡ ፡ ፩
በደስታ ፡ ቃልም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እልል ፡ በሉ ።
እግዚአብሔር ፡ ልዑል ፡ ግሩምም ፡ ነውና ፡ ፪
በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይም ፡ ታላቅ ፡ ንጉሥ ፡ ነውና ።
አሕዛብን ፡ ከእኛ ፡ በታች ፡ ፫
ወገኖችንም ፡ ከእግራችን ፡ በታች ፡ አስገዛልን ።
የያዕቆብን ፡ ውበት ፡ የወደደ ፡ እርሱ ፡ ፬
ለርስቱ ፡ እኛን ፡ መረጠን ።
አምላክ ፡ በእልልታ ፡ ወደሰማይ ፡ ወጣ ፡ ፭
እግዚአብሔር ፡ በመለከት ፡ ድምፅ ፡ ዐረገ ። ፮
ዘምሩ ፡ ለአምላካችን ፡ ዘምሩ ፡
ዘምሩ ፡ ለንጉሣችን ፡ ዘምሩ ።
እግዚአብሔር ፡ ለምድር ፡ ሁሉ ፡ ንጉሥ ፡ ነውና ፡ ፯
በማስተዋል ፡ ዘምሩ ።
እግዚአብሔር ፡ በአሕዛብ ፡ ላይ ፡ ነገሠ ፡ ፰
እግዚአብሔር ፡ በቅድስናው ፡ ዙፋን ፡ ይቀመጣል ።
የምድር ፡ ኃይለኞች ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ናቸውና ፡ ፱
የአሕዛብ ፡ አለቆች ፡ ወደ ፡ አብርሃም ፡ አምላክ ፡ ተሰበሰቡ ፡
እርሱንም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረጉት ።

መዝሙር ፡ ፵፰ ።

ስለ ፡ ሕዝቅያስ ።

እግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፡ ነው ፡ ፩
በአምላካችን ፡ ከተማ ፡ በተቀደሰውም ፡ ተራራ ፡
ምስጋናው ፡ የበዛ ፡ ነው ።

፪ አድባረ ፡ ጽዮን ፡ በገቦ ፡ መስዕ ።
ሀገሩ ፡ ለንጉሥ ፡ ዐቢይ ።
፫ እግዚአብሔር ፡ የአምር ፡ ክበዲሃ ፡ ሶበ ፡ ተመጠውዋ።
፬ እስመ፡ናሁ፡ነገሥት፡ምድር፡ተጋብኡ፡ወመጽኡ፡ኅቡረ።
፭ እሙንቱሰ ፡ ዘንተ ፡ ርእዮሙ ፡ አንከሩ ።
፮ ደንገፁ ፡ ወፈርሁ ፡ ወአኀዞሙ ፡ ረዓድ ።
ወሐሙ ፡ በህየ ፡ ከመ ፡ እንተ ፡ ትወልድ ።
፯ በነፋስ ፡ ኀያል ፡ ትቀጠቅጦን ፡ ለአሕማረ ፡ ተርሴስ ።
፰ በከመ ፡ ሰማዕነ ፡ ከማሁ ፡ ርኢነ ።
በሀገረ ፡ እግዚአ ፡ ኀያላን ፡ በሀገረ ፡ አምላክነ ።
እግዚአብሔር ፡ ሣረራ ፡ ለዓለም ።
፱ ተወከፍነ ፡ እግዚኦ ፡ ሣህለከ ፡ በማእከለ ፡ ሕዝብከ ።
፲ ወበከመ ፡ ስምከ ፡ ከማሁ ፡ ስብሐቲከ ፡ በኲሉ ፡ አጽናፈ፡ምድር ።
ጽድቀ ፡ ምሉዕ ፡ የማንከ ።
፲፩ ይትፌሣሕ ፡ አድባረ ፡ ጽዮን ።
ወይትሐሠያ ፡ አዋልደ ፡ ይሁዳ ።
በእንተ ፡ ፍትሕከ ፡ እግዚኦ ።
፲፪ ዕግትዋ ፡ ለጽዮን ፡ ወሕቀፍዋ ።
ወተናገሩ ፡ በውስተ ፡ማኅፈዲሃ ።
፲፫ ደዩ ፡ ልበክሙ ፡ ውስተ ፡ ኀይላ ።
ወትትካፈልዎ ፡ለክበዲሃ ።
ከመ ፡ ትንግሩ ፡ ለካልእ ፡ ትውልድ ።
፲፬ ከመ ፡ ዝንቱ ፡ ውእቱ ፡ አምላክነ ።
ለዓለም ፡ ወለዓለመ ፡ ዓለም ።
ወውእቱ ፡ ይርዕየነ ፡ እስከ ፡ ለዓለም ።



በሰሜን። ወገን ፡ በመልካም ፡ ስፍራ ፡ የቆመ ፡ ፪
የምድር ፡ ሁሉ ፡ ደስታ ፡ የጽዮን ፡ ተራራ ፡ ነው ።
እርሱም ፡ የታላቁ ፡ ንጉሥ ፡ ከተማ ፡ ነው ።
እግዚአብሔር ፡ በአዳራሾቿ፡መጠጊያ፡ሆኖ፡ይታወቃል ። ፫
እነሆ፡ነገሥታት፡ተከማችተው፡በአንድነት፡መጥተዋል ። ፬
እነርሱስ ፡ አይተው ፡ ተደነቁ ፡ ደነገጡ ፡ ታወኩ ። ፭
ተንቀጠቀጡ፡ እንደ፡ ወላድም፡ ምጥ፡ በዚያ፡ ያዛቸው ። ፮
በኃይለኛ ፡ ነፋስ፡ የተርሴስን ፡ መርከቦች፡ ትሰብራለህ ። ፯
እንደ ፡ ሰማን ፡ እንዲሁ ፡ አየን ። ፰
በሠራዊት ፡ ጌታ ፡ አገር ፡ በአምላካችን ፡ ከተማ ፤
እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ ያጸናታል ።
አምላክ ፡ ሆይ ፡ በሕዝብህ ፡ መካከል ፡ ምሕረትህን ፡ ተቀበልን ። ፱
አምላክ ፡ ሆይ ፡ እንደ ፡ ስምህ ፤ ፲
እንዲሁም ፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ ምስጋናህ ፡ የመላ ፡ ነው ፤
ቀኝህም ፡ ጽድቅን ፡ የተመላች ፡ ናት ።
አቤቱ ፡ ስለ፡ፍርድህ፡ የጽዮን ፡ ተራራ ፡ ደስ ፡ ይበለው ፤ ፲፩
የአይሁድም ፡ ሴት ፡ ልጆች ፡ ሐሤትን ፡ ያድርጉ ።
ጽዮንን ፡ ክበቡአት ፡ በዙሪያዋም ፡ ተመላለሱ ፤ ፲፪
ግንቦችዋንም ፡ ቍጠሩ ፤
በብርታትዋ ፡ የልባችሁን ፡ ተስፋ ፡ አኑሩ ፤ ፲፫
አዳራሾዋን ፡ ተመልከቱ ፤
ለሚመጣው ፡ ትውልድ ፡ ትነግሩ ፡ ዘንድ ፡ እስቡ ።
ለዓለምና ፡ ለዘላለም ፡ ይህ ፡ አምላካችን ፡ነው ፤ ፲፬
እርሱም ፡ ለዘላለም ፡ ይመራናል ።

መዝሙር ፡ ፵፰ ።

ተግሣጽ ፡ ለኲሉ ።

፩ ስምዑ ፡ ዘንተ ፡ ኲልክሙ ፡ አሕዛብ ።
ወአጽምዑ፡ኲልክሙ ፡ እለ ፡ ትነብሩ ፡ ውስተ ፡ ዓለም ።
በበ ፡ በሐውርቲክሙ ፡ ደቂቀ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ።
፪ አብዕልትኒ ፡ ወነዳይኒ ።
፫ አፉየ ፡ የነግር ፡ ጥበበ ።
ወሕሊና ፡ ልብየ ፡ ምክረ ።
፬ አጸምዕ ፡ ምሳሌ ፡ በእዘንየ ።
ወእከሥት ፡ በመዝሙር ፡ ነገርየ ።
ለምንት ፡ እፈርህ ፡ እምዕለት ፡ እኪት ።
፭ ኀጢአት ፡ ሰኰናየ ፡ አገተኒ ።
፮ እለ ፡ ይትአመኑ ፡ በኀይሎሙ ።
ወይዜኀሩ ፡ በብዝኀ ፡ ብዕሎሙ ።
፯ እኁኒ ፡ ኢያድኅን ፡ እኁዋሁ ፡ ወኢያድኅን ፡ ሰብእ ።
፰ ወኢይሁብ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቤዛሁ ።
፱ ወኢተውላጠ ፡ ሤጠ ፡ ነፍሱ ።
ዘፃመወ ፡ በዓለም ፡ የሐዩ ፡ ለዝሉፉ ።
እስመ ፡ ኢይሬኢ ፡ ሙስና ።
፲ ሶበ ፡ ትሬእዮሙ ፡ ለጠቢባን ፡ ይመውቱ ።
ወከማሁ ፡ ይትሀጐሉ ፡ አብዳን ፡ እለ ፡ አልቦሙ ፡ ልብ
ወየኀድጉ ፡ ለባዕድ ፡ ብዕሎሙ ።
፲፩ መቃብሪሆሙ ፡ ወአብያቲሆሙ ፡ ለዓለም ።
ወማኅደሪሆሙኒ ፡ ለትውልደ ፡ ትውልድ ።
ወይሰመይ ፡ አስማቲሆሙ ፡ በበ ፡ በሐውርቲሆሙ ።
፲፪ ሰብእሰ ፡ እንዘ ፡ ክቡር ፡ ውእቱ ፡ ኢያእመረ ።
ወኮነ ፡ ከመ ፡ እንስሳ ፡ ዘአልቦ ፡ ልብ ፡ ወተመሰሎሙ።
፲፫ ወለሊሃ ፡ ፍኖቶሙ ፡ ዕቅፍቶሙ ።
እንዘ ፡ ይሠምሩ ፡ በአፉሆሙ ።

መዝሙር ፡ ፵፰ ።

ተግሣጽና ፡ ምክር ፡ ለሁሉም ።

አሕዛብ ፡ ሁላችሁ ፡ ይህን ፡ ስሙ ፤ ፩
በዓለም ፡ የምትኖሩም ፡ ሁላችሁ ፡ አድምጡ ።
ዝቅተኞችና ፡ ከፍተኞች ፤ ፪
ባለጠጎችና ፡ ድሆች ፡ በአንድነት ፡ ስሙ ።
አፌ ፡ ጥበብን ፡ ይናገራል ፤ ፫
የልቤም ፡ አሳብ ፡ ማስተዋልን ፡ ይቀኛል ።
ጆሮዬን ፡ ወደ ፡ ምሳሌ ፡ አዘነብላለሁ ፤ ፬
በበገናም ፡ ምሥጢሬን ፡ እገልጣለሁ ።
ኃጢአት ፡ ተረከዜን ፡ በከበበኝ ፡ ጊዜ ፤ ፭
በክፉ ፡ ቀን ፡ ለምን ፡ እፈራለሁ ። ?
በኃይላቸው ፡ የሚታመኑ ፤ ፮
በባለጠግነታቸውም ፡ ብዛት ፡ የሚመኩ ።
ወንድም ፡ወንድሙን፡ አይታደግም፡ሰውም፡ አያድንም ። ፯
ለዘላለም ፡ እንዲኖር ፡ ጥፋትንም ፡ እንዳያይ ፤ ፰
ቤዛውን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አይሰጥም ።
የነፍሳቸው ፡ ለውጥ ፡ ከብሮአልና ፤ ፱
ለዘላለምም ፡ ቀርቶአልና ።
ብልሃተኞች ፡ እንዲሞቱ ፤ ፲
ሰነፎችና ፡ ደንቆሮች ፡ በአንድነት ፡ እንዲጠፉ ፤
ገንዘባቸውንም ፡ ለሌሎች ፡ እንዲተዉ ፡ አይቶአል ።
በልባቸውም ፡ ቤታቸው ፡ ለዘላለም ፡ የሚኖር ፤ ፲፩
ማደሪያቸውም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ፡ የሚሆን፡ ይመስላቸዋል ፤
በየአገራቸውም ፡ ስማቸው ፡ ይጠራል ።
ሰው ፡ ግን ፡ ክቡር ፡ ሆኖ ፡ ሳለ ፡ አያውቅም ፤ ፲፪
እንደሚጠፉ ፡ እንስሶችም ፡ መሰለ ።
ይህች ፡ መንገዳቸው ፡ መሰናክላቸው ፡ ናት ፤ ፲፫
ከእነርሱም፡ በኋላ፡ የሚመጡ፡ በአፋቸው፡ እሺ፡ ይላሉ ።

፲፬ ከመ ፡ አባግዕ ፡ ሞት ፡ ይርዕዮሙ ፡ በሲኦል ።
ወይቀንይዎሙ ፡ ራትዓን ፡ በጽባሕ ።
ወትበሊ ፡ ረድኤቶሙ ፡ በሲኦል ፡ እምክብሮሙ ።
፲፭ ወባሕቱ ፡ እግዚአብሔር ፡ያድኅና ፡ ለነፍስየ ፡ እምእደ
ሲኦል ፡ ሶበ ፡ ይነሥኡኒ ።
፲፮ ኢትፍርሆ ፡ ለሰብእ ፡ ሶበ ፡ ይብዕል ።
ወሶበ ፡ ይበዝኅ ፡ ክብረ ፡ ቤቱ ።
፲፯ እስመ ፡ ኢይነሥእ ፡ ምስሌሁ ፡ ኵሎ ፡ አመ ፡ ይመውት
ወኢይወርድ ፡ ምስሌሁ ፡ ኵሉ ፡ ክብረ ቤቱ ፡ ።
፲፰ እስመ ፡ ፈግዐት ፡ ነፍሱ ፡ በሕይወቱ ።
የአምነከ ፡ ሰብእ ፡ ሶበ ፡ ታሤኒ ፡ ሎቱ ።
፲፱ ወይወርድ ፡ ውስተ ፡ ዓለመ ፡ አበዊሁ ፡
ወኢይሬኢ ፡ እንከ ፡ ብርሃነ ፡ እስከ ፡ ለዓለም ።
፳ ዕጓለ ፡ እመሕያው፡እንዘ፡ክቡር፡ውእቱ፡ኢያእመረ ።
ወኮነ ፡ ከመ፡ እንስሳ ፡ ዘአልቦ ፡ ልብ ፡ ወተመሰሎሙ ።

መዝሙር ፡ ፵፱ ።

በእንተ ፡ ዘለፋ ፡ ካህናት ።

፩ አምላከ አማልክት ፡ እግዚአብሔር ነበበ ፡ ወጸውዓ ፡ ለምድር ።
እምሥራቀ ፡ ፀሐይ ፡ እስከነ ፡ ዓረብ ።
፪ እምጽዮን ፡ ሥነ ፡ ስብሐቲሁ ።
እግዚአብሔርሰ ፡ ገሃደ ፡ ይመጽእ ።
፫ ወአምላክነሂ ፡ ኢያረምም ።
እሳት ፡ ይነድድ ፡ ቅድሜሁ ።
ዐውዶሂ ፡ ዐውሎ ፡ ብዙኅ ።
፬ ይጼውዓ ፡ ለሰማይ ፡ በላዕሉ ።
ወለምድርኒ ፡ ከመ ፡ ይኰንን ፡ ሕዝቦ ።
አስተጋብኡ ፡ ሎቱ ፡ ጻድቃኑ ።
፭ እለ ፡ ይገብሩ ፡ መሥዋዕተ ፡ ዘበሕጉ ።
፮ ይነግሩ ፡ ሰማያት ፡ ጽድቀ ፡ ዚአሁ ።
እስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ መኰንን ፡ ውእቱ ።
፯ ስምዐኒ ፡ ሕዝብየ ፡ ወእንግርከ ።
እስራኤል ፡ አሰምዕ ፡ ለከ ።
አምላክከሰ ፡ አምላክ ፡ አነ ፡ ውእቱ ።
፰ አኮ ፡ በእንተ ፡ መሥዋዕቲከ ፡ ዘእዛለፈከ ።
ወቍርባንከኒ ፡ ቅድሜየ ፡ ውእቱ ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ።
፱ ኢይነሥእ ፡ አልሕምተ ፡ እምቤትከ ።
ወኢሐራጊተ ፡ እመርዔትከ ።
፲ እስመ ፡ ዚአየ ፡ ውእቱ ፡ ኵሉ ፡ አራዊት ፡ ዘገዳም ።
እንስሳ ፡ ገዳምኒ ፡ ወአልሕምት ።
፲፩ ወአአምር ፡ ኵሎ ፡ አዕዋፈ ፡ ሰማይ ።
ወሥነ ፡ ገዳምኒ ፡ ኀቤየ ፡ ሀሎ ።
እመኒ ፡ ርኅብኩ ፡ ኢይስእለከ ።
፲፪ እስመ ፡ ዚአየ ፡ ውእቱ ፡ ኵሉ ፡ ዓለም ፡ በምልኡ ።
፲፫ ኢይበልዕ ፡ ሥጋ ፡ ላሕም ፡ ወኢይሰቲ ፡ ደመ ፡ ጠሊ ።
፲፬ ሡዕ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መሥዋዕተ ፡ ስብሐት ።
ወሀቦ ፡ ለልዑል ፡ ጸሎተከ ።
፲፭ ትጼውዐኒ ፡ በዕለተ ፡ ምንዳቤከ፡ አድኅነከ፡ ወተአኵተኒ
፲፮ ወለኃጥእሰ ፡ ይቤሎ ፡ እግዚአብሔር ።
ለምንት ፡ ለከ ፡ ትነግር ፡ ሕግየ ።
ወትነሥእ ፡ በአፉከ ፡ ሥርዓትየ ።
፲፯ ወአንተሰ ፡ ጸላእከ ፡ ተግሣጽየ ።
ወአግባእከ ፡ ድኅሬከ ፡ ቃልየ ።
፲፰ እመኒ ፡ ርኢከ ፡ ሠራቄ ፡ ትረውጽ ፡ ምስሌሁ ።
ወረሰይከ ፡ መክፈልተከ ፡ ምስለ ፡ ዘማውያን ።
፲፱ አፉከ ፡ አብዝኀ ፡ ለእኪት ።
ወልሳንከ ፡ ፀፈረ ፡ ለሕብል ።



እንደ ፡ በጎች ፡ ወደ ፡ ሲኦል ፡ የሚሄዱ ፡ ናቸው ፡ ፲፬
እረኛቸውም ፡ ሞት ፡ ነው ፤
ቅኖችም ፡ በማለዳ ፡ ይገዙአቸዋል ፡ ውበታቸውም ፡
ከመኖሪያቸው ፡ ተለይታ ፡ በሲኦል ፡ ታረጃለች ።
ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ይቀበለኛልና ፡ ፲፭
ነፍሴን ፡ ከሲኦል ፡ እጅ ፡ ይዋጃታል ።
የሰው፡ ባለጠግነት፡ የቤቱም ፡ ክብር፡ ቢበዛ፡ አትፍራ ፡ ፲፮
በሞተ ፡ ጊዜ ፡ ከእርሱ ጋር ፡ምንም ፡ አይወስድምና ፡ ፲፯
ክብሩም ፡ ከእርሱ ፡ በኋላ ፡ አይወርድምና ።
በሕይወቱ ፡ ሳለ ፡ ሰውነቱን ፡ አስደስቷልና ፤ ፲፰
ለሰውነቱ ፡ መልካም ፡ ብታደርግለት ፡ ያመሰግንሃል ።
ሆኖም ፡ ወደ ፡ አባቶቹ ፡ ትውልድ ፡ ይወርዳል ፤ ፲፱
ለዘላለም ፡ ብርሃንን ፡ አያይም ።
ሰው ፡ ክቡር ፡ ሆኖ ፡ ሳለ ፡ አእምሮ ፡ እንደሌለው ፡ ፳
እንደሚጠፉ ፡ እንስሶች ፡ መሰለ ።

መዝሙር ፡ ፵፱ ።

ስለ ፡ ካህናት ፡ ዘለፋ ።

የአማልክት ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፩
ተናገረ ፡ ከፀሐይም ፡ መውጫ ፡ ጀምሮ ፡
እስከ ፡ መግቢያዋ ፡ ድረስ ፡ ምድርን ፡ ጠራት ።
ከክብሩ ፡ ውበት ፡ ከጽዮን ፡ ፪
እግዚአብሔር ብግልጽ ፡ ሆኖ ፡ ይመጣል ።
አምላካችን ፡ ይመጣል ፡ ዝምም ፡ አይልም ፤ ፫
እሳት ፡ በፊቱ ፡ ይነዳል ፤
በዙሪያውም ፡ ብዙ ፡ ዐውሎ ፡ አለ ።
በላይ ፡ ያለውን ፡ ሰማይን ፤ ፬
ምድርንም ፡ በሕዝቡ ፡ ለመፍረድ ፡ ይጠራል ።
ከእርሱ፡ ጋራ፡ ለመሥዋዕት፡ ኪዳን፡ የቆሙትን፡ቅዱሳኑን፡ሰብስቡለት፡ ፭
ሰማያት ፡ ጽድቁን ፡ ይናገራሉ ፤ ፮
እግዚአብሔር ፡ ፈራጅ ፡ ነውና ።
ሕዝቤ ፡ ሆይ ፡ ስማኝ ፡ ልንገርህ ፤ ፯
እስራኤልም ፡ ስማኝ ፡ ልመስክርብህ ፤
አምላክስ ፡ እኔ ፡ አምላክህ ፡ ነኝ ።
ስለ ፡ ቍርባንህ ፡ የምዘልፍህ ፡ አይደለሁም ፤ ፰
የሚቃጠል ፡ መሥዋዕትህ ፡ ሁል ፡ ጊዜ፡በፊቴ፡ነው ።
የምድረ በዳ አራዊት ሁሉ በሺህ ተራራዎች ያሉ እንስሶችም የእኔ ናቸውና ፱
ከቤትህ ፡ የሰባ ፡ ፍሪዳን ፡ ፲
ከመንጋህም ፡ አውራ ፡ ፍየልን ፡ አልወስድም ።
የሰማይን ፡ አዕዋፍ ፡ ሁሉ ፡ አውቃለሁ ፤ ፲፩
የምድረ ፡ በዳ ፡ አራዊትም ፡ በእጄ ፡ ናቸው ።
ብራብም ፡ ለአንተ ፡ አልነግርህም ፤
ዓለም ፡ በመላው ፡ የእኔ ፡ ነውና ። ፲፪
የፍሪዳውን ፡ ሥጋ ፡ እበላለሁን ? ፲፫
የፍየሉንስ ፡ ደም ፡ እጠጣለሁን ?
ለእግዚአብሔር ፡ የምስጋናን ፡ መሥዋዕት ፡ ሠዋ ፤ ፲፬
ለልዑልም ፡ ስእለትህን ፡ ስጥ ።
በመከራህ ፡ ቀን ፡ ጥራኝ፡ አድንሃለሁ ፤ ፲፭
አንተም ፡ ታከብረኛለህ ።
ኃጢአተኛውን፡ግን ፡እግዚአብሔር ፡ እንዲህ፡አለው ፤ ፲፮
ለምን ፡ አንተ ፡ ሕጌን ፡ ትናገራለህ ?
ኪዳኔንም ፡ በአፍህ ፡ ለምን ፡ ታወራለህ ?
አንተስ ፡ ተግሣጼን ፡ ጠላትህ ፡ ፲፯
ቃሎቼን ፡ ወደኋላህ ፡ ጥለኸልና ።
ሌባውን፡ ባየህ፡ ጊዜ፡ ከእርሱ፡ ጋር፡ ትሮጣለህ ፡ ፲፰
እድል ፡ ፈንታህንም ፡ ከአመንዝሮች፡ጋር፡አደረግህ ።
አፍህ ፡ ክፋትን ፡ አበዛ ፤ ፲፱
እንደበትህም ፡ ሽንገላን ፡ ተበተበ ።

፯ ወአውዐዩ ፡ በእሳት ፡ መቅደሰከ ።
ወአርከሱ ፡ ማኅደረ ፡ ስምከ ፡ ውስተ ፡ ምድር ።
፰ ወይቤሉ ፡ በልቦሙ ፡ ኀቢሮሙ ፡ በበ ፡ ሕዝቢሆሙ ።
ንዑ፡ንስዐር፡ኵሎ፡በዓላቲሁ፡ ለእግዚአብሔር፡ እምድር
፱ ወትእምርቶሂ ፡ ኢነአምር ።
ወአልቦ ፡ እንከ ፡ ነቢይ ።
ወንሕነሂ ፡ ኢነአምር ፡ እንከ ።
፲ እስከ ፡ ማእዜኑ ፡ እንከ ፡ እግዚኦ ፡ ይጼዕል ፡ ፀራዊ ።
ወዘልፈ ፡ ያምዕዖ ፡ ለስምከ ፡ ጸላዒ ።
ለምንት ፡ እግዚኦ ፡ ትመይጥ ፡ እዴከ ።
፲፩ ወየማንከ ፡ ማእከለ ፡ ሕፅንከ ፡ ለግሙራ ።
፲፪ እግዚአብሔርሰ ፡ ንጉሥ፡ውእቱ፡ እምቅድመ፡ ዓለም።
ወገብረ ፡ መድኀኒተ ፡ በማእከለ ፡ ምድር ።
፲፫ አንተ ፡ አጽናዕከ ፡ ለባሕር ፡ በኀይልከ ።
ወአንተ ፡ ሰበርከ ፡ ርእሰ ፡ ከይሲ ፡ በውስተ ፡ ማይ ።
፲፬ ወአንተ ፡ ቀጥቀጥከ ፡ አርእስቲሁ ፡ ለከይሲ ።
ወወሀብኮሙ ፡ ሲሳዮሙ ፡ ለሕዝበ ፡ ኢትዮጵያ ።
፲፭ አንተ ፡ ሠጠቀ ፡ አፍላገ ፡ ወአንቅዕተ ።
፲፮ ለከ ፡ ውእቱ ፡ መዓልት ፡ ወዚአከ ፡ ይእቲ ፡ ሌሊት ።
አንተ ፡ ፈጠርከ ፡ ፀሐየ ፡ ወወርኀ ።
፲፯ ወአንተ ፡ ገበርከ ፡ አድባረ ፡ ወምድረ ፡ ኵሎ ።
ክረምተ ፡ ወሐጋየ ፡ ዘአንተ ፡ ፈጠርከ ።
፲፰ ወተዘከር ፡ ዘንተ ፡ ተግባረከ ።
ፀራዊ ፡ ተዐየሮ ፡ ለእግዚአብሔር ።
ወሕዝብ ፡ አብድ ፡ አምዐዖ ፡ ለስሙ ።
፲፱ ኢትመጥዋ ፡ ለአራዊት ፡ ለነፍስ ፡ እንተ ፡ ትገኒ ፡ ለከ ።
ወኢትርሳዕ ፡ ነፍሰ ፡ ነዳያኒከ ፡ ለዝሉፉ ።
፳ ወነጽር ፡ ውስተ ፡ ሥርዐትከ ።
እስመ ፡ በዝኁ ፡ ጽሉማነ ፡ ምድር ፡ አብያተ ፡ ኃጥኣን።
፳፩ ኢይግባእ ፡ ነዳይ ፡ ተኀፊሮ ።
ነዳይ ፡ ወምስኪን ፡ ይሴብሑ ፡ ለስምከ ።
፳፪ ተንሥእ ፡ እግዚኦ ፡ ወተበቀል ፡ በቀልየ ።
ወተዘከር ፡ ዘተዐየሩከ ፡ አብዳን ፡ ኵሎ ፡ እሚረ ።
፳፫ ወኢትርሳዕ ፡ ቃለ ፡ እግብርቲከ ።
ትዝኅርቶሙ፡ ለጸላእትከ፡ ይዕርግ፡ ኀቤከ፡በኵሉ፡ጊዜ ።

መዝሙር ፡ ፸፬ ።

በእንተ ሕዝቅያስ ።

፩ እገኒ ፤ ለከ ፡ እግዚኦ ፡ እገኒ ፡ ለከ ።
እገኒ ፡ ለከ ፡ ወእጼውዕ ፡ ስመከ ።
ወእነግር ፡ ኵሎ ፡ ስብሐቲከ ።
፪ ሶበ ፡ ረከብኩ ፡ ጊዜሁ ።
ወአንሰ ፡ ጽድቀ ፡ እኬንን ።
፫ ተመስወት ፡ ምድር፡ወኵሎሙ፡እለ፡ይነብሩ፡ውስቴታ።
ወአነ ፡ አጽናዕኩ ፡ አዕማዲሃ ።
፬ ወእቤሎሙ ፡ ለኃጥኣን ፡ ኢይኤብሱ ።
ወእለሂ ፡ ይኤብሱ ፡ ኢያንሥኡ ፡ ቀርኖሙ ።
፭ ወኢያንሥኡ ፡ ቀርኖሙ ፡ ውስተ ፡ አርያም ።
ወኢይንብቡ ፡ ዐመፃ ፡ ላዕለ ፡ እግዚአብሔር ።
፮ እስመ ፡ ኢእምጽባሕ ፡ ወኢእምዓረብ ፡ ወኢእምአ
ድባረ ፡ ገዳም ።
፯ እስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ መኰንን ፡ ውእቱ ።
ዘንተ ፡ ያኀስር ፡ ወዘንተ ፡ ያከብር ።
፰ እስመ ፡ ጽዋዕ ፡ ውስተ ፡ እዴ ፡ እግዚአብሔር ፡
ወይን ፡ ዘኢኮነ ፡ ቱሱሐ ፡ ወምሉዕ ፡ ቅድሒተ ።
ወሶጠ ፡ እምዝንቱ ፡ ውስተ ፡ ዝንቱ ።
ወባሕቱ ፡ ጣሕሉኒ ፡ ኢይትከዐው ።
ወይሰትይዎ ፡ ኵሎሙ ፡ ኃጥኣነ ፡ ምድር ።



መቅደስህን ፡ በእሳት ፡ አቃጠሉ ፡ ፯
የስምህንም ፡ ማደሪያ ፡ በምድር ፡ ውስጥ ፡ አረከሱ ።
ልባቸውን ፡ አንድ ፡ አድርገው ፡ ፰
ሕዝባቸውን ፡ አስተባብረው ፡
ኑ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ በዓሎች፡ ከምድር፡ እንሻር፡ አሉ።
ምልክታችንን፡አናይም፡ከእንግዲህ፡ወዲህም፡ነቢይ፡የለም ፱
እስከ፡መቼ፡እንዲኖር፡የሚያውቅ፡ በኛ፡ዘንድ፡ይህ፡ የለም ።
አቤቱ ፡ ጠላት ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ይሳደባል ? ፲
እስከ ፡ መቼስ ፡ ስምህን ፡ ሁልጊዜ ፡ ያቃልላል ?
ቀኝህን ፡ በብብትህ ፡ መካከል ፡ ፲፩
እጅህንም ፡ ፈጽመህ ፡ ለምን ፡ ትመልሳለህ ፡
እግዚአብሔር ፡ ግን፡ ከዓለም፡ አስቀድሞ፡ ንጉሥ፡ነው ፲፪
በምድርም ፡ መካከል ፡ መድኃኒትን ፡ አደረገ ።
አንተ ፡ ባሕርን ፡ በኃይልህ ፡ አጸናሃት ፡
አንተ ፡ የአባቦችን ፡ ራስ፡ በውኃ ፡ ውስጥ፡ ቀጠቀጥህ ።
የዘንዶውንም ፡ ራስ ፡ ፈጠፈጥህ ፡ ፲፬
ለኢትዮጵያ ፡ ሰዎች ፡ ምግባቸውን ፡ ሰጠሃቸው ።
አንተ፡ ምንጮቹንና ፡ ፈሳሾቹን ፡ ሰነጠቅህ ፡ ፲፭
አንተ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ የሚፈሱትን ፡ ወንዞች ፡ አደረቅህ ።
ቀኑ ፡ የአንተ ፡ ነው ፡ ሌሊቱም ፡ የአንተ ፡ ነው ፡ ፲፮
አንተ ፡ ፀሐዩንና ፡ ጨረቃውን ፡ አዘጋጀህ ።
አንተ ፡ የምድርን ፡ ዳርቻ ፡ ሁሉ ፡ ሠራህ ፡ ፲፯
በጋንም ፡ ክረምትንም ፡ አንተ ፡ ፈጠርህ ።
ይህን ፡ ፍጥረትህን ፡ አስብ ፡ ፲፰
ጠላት እግዚአብሔርን ፡ ተላገደ ፡
ሰነፍ ፡ ሕዝብም ፡ ስሙን ፡ አስቆጣ ።
የምትገዛልህን፡ነፍስ፡ለአራዊት፡አሳልፈህ፡ አትስጣት ፤ ፲፱
የችግረኞችህን ፡ ነፍስ ፡ ለዘወትር ፡ አትርሳ ።
ወደ ፡ ኪዳንህ ፡ ተመልከት ፤ ፳
በምድር ፡ የጨለማ ፡ ስፍራዎች ፡ በኃጥአን ፡ ቤቶች ፡ ተመልተዋልና ።
ችግረኛ ፡ አፍሮ ፡ አይመለስ ፡ ፳፩
ችግረኛና ፡ ምስኪን ፡ ስምህን ፡ ያመሰግናሉ ።
አቤቱ ፡ ተነሥ ፡ በቀልህንም ፡ ተበቀል ፡ ፳፪
ሰነፎች ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ የተላገዱህን ፡ አስብ ።
የባሪያዎችህን ፡ ቃል ፡ አትርሳ ፡ ፳፫
የጠላቶችህ፡ኩራት፡ ሁል፡ጊዜ፡ ወደ፡አንተ፡ ይወጣልና ።

መዝሙር ፡ ፸፬ ።

ስለ ሕዝቅያስ ።

አቤቱ ፡ እናመሰግንሃለን ፡ ፩
እናመሰግንሃለን ፡ ስምህንም ፡ እንጠራለን ፡
ተአምራትህን ፡ ሁሉ ፡ እናገራለሁ ።
ጊዜው ፡ ሲገጥመኝ ፡ እኔ ፡ በቅን ፡ እፈርዳለሁ ፡ ፪
ምድርና፡ በእርሷ ፡ ውስጥ ፡ የሚኖሩት፡ ሁሉ ፡ ቀለጡ ፡ ፫
እኔም ፡ ዓምዶቿን ፡ አጸናሁ ።
ዓመፀኞችን ፡ አትበድሉ ፡ አልኋቸው ፡ ፬
ኃጢአተኞችንም ፡ ቀንዳችሁን ፡ አታንሡ ።
ቀንዳችሁን ፡ እስከ ፡ ላይ ፡ አታንሡ ፡ ፭
በእግዚአብሔርም ፡ ላይ ፡ ዓመፅን ፡ አትናገሩ ።
ክብር ፡ ከምሥራቅ ፡ ወይም ፡ ከምዕራብ ፡ ወይም ፡
ከምድረ ፡ በዳ ፡ የለምና ፡ ፮
እግዚአብሔር ፡ ፈራጅ ፡ ነውና ። ፯
ይህን ፡ ያዋርዳል ፡ ያንንም ፡ ያከብራል ።
ጽዋ ፡ በእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ ነውና ፡ ፰
ያልተቀላቀለ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ሞላበት ፡
ከዚህ ፡ ወደዚያ ፡ አገላበጠው ።
ነገር ፡ ግን ፡ አተላው ፡ አልፈሰሰም ፡
የምድር ፡ ኃጢአተኞች ፡ ሁሉ ፡ ይጠጡታል ።

፱ ወአንሰ ፡ እትፌሣሕ ፡ ለዓለም ።
ወእዜምር ፡ ለአምላከ ፡ ያዕቆብ ።
፲ ወእሰብር ፡ አቅርንቲ ፡ ኃጥአን ።
ወይትሌዐል ፡ አቅርንቲ ፡ ጻድቃን ።

መዝሙር ፡ ፸፭ ።

በእንተ ሕዝቅያስ ።

፩ ተዐውቀ ፡ እግዚአብሔር ፡ በይሁዳ ።
ወዐቢየ ፡ ስሙ ፡ በእስራኤል ።
፪ ወነበረ ፡ በሰላም ፡ ብሔሮ ፡
ወማኅደሩኒ ፡ ውስተ ፡ ጽዮን ።
፫ ወበህየ ፡ ሰበረ ፡ ኀይለ ፡ ቀስት ።
ወልታ ፡ ወኲናተ ፡ ወጸባኢተ ።
ወበህየ ፡ ሰበረ ፡ አቅርንተ ።
፬ አንተ ፡ ታበርህ ፡ መንክረ ።
እምአድባር ፡ ዘለዓለም ።
፭ ደንገጹ ፡ ኵሎሙ ፡ አብዳን ፡ ልብ ።
ሐለሙ ፡ ሕልመ ፡ ወአልቦ ፡ ዘረከቡ ።
ኵሉ ፡ ሰብአ ፡ ለብዕለ ፡ እደዊሆሙ ።
፮ እምተግሣጽከ ፡ አምላከ ፡ ያዕቆብ ።
ደቀሱ ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይጼዐኑ ፡ አፍራሰ ።
፯ አንተሰ ፡ ግሩም ፡ አንተ ።
ወመኑ ፡ ይትቃወም ፡ ለመዓትከ ።
፰ እምሰማይ ፡ ታጸምዕ ፡ ፍትሐ ።
ምድርኒ ፡ ፈርሀት ፡ ወአርመመት ።
ሶበ ፡ ተንሥአ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለኰንኖ ።
፱ ከመ ፡ ያድኅኖሙ ፡ ለኵሎሙ ፡ የዋሃነ ፡ ልብ ።
፲ እስመ ፡ እምፈቃዱ ፡ የአምነከ ፡ ሰብእ ።
ወእምተረፈ ፡ ኀሊናሆሙ ፡ ይገብሩ ፡ በዓለከ ።
፲፩ ብፅዑ ፡ ወሀቡ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አምላክነ ።
ኵሎሙ ፡ እለ ፡ ዐውዱ ፡ ያበውኡ ፡ አምኃ ።
፲፪ ለግሩም ፡ ዘያወጽእ ፡ ነፍሶሙ ፡ ለመላእክት ።
ወይጌርም ፡ እምነገሥተ ፡ ምድር ።

መዝሙር ፡ ፸፮ ።

ተግሣጽ ፡ ለዘሉ ።

፩ ቃልየ ፡ ኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸራኅኩ ።
ቃልየ ፡ ኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡ አጽምዐኒ ።
፪ በዕለተ ፡ ምንዳቤየ ፡ ኀሠሥክዎ ፡ ለእግዚአብሔር ።
እደውየ ፡ ሌሊተ ፡ ቅድሜሁ ፡ ወኢኬዱኒ ።
ቀብጸት ፡ ነፍስየ ፡ ትፍሥሕተ ።
፫ ተዘከርክዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ወተፈሣሕኩ ።
ተዛዋዕኩኒ ፡ ወአንበዘት ፡ ነፍስየ ።
፬ ተራከብክዎን ፡ ለሰዓታተ ፡ ኵሎሙ ፡ ጸላእትየ ።
ደንገጽኩኒ ፡ ወኢነበብኩ ።
፭ ወሐለይኩ ፡ መዋዕለ ፡ ትካት ።
ተዘከርኩ ፡ ዓመተ ፡ ዓለም ፡ ወአንበብኩ ።
፮ ሌሊተ ፡ ተዛዋዕኩ ፡ ምስለ ፡ ልብየ ፡ ወአንቃሕክዋ
ለነፍስየ ።
፯ ቦኑ ፡ ለዓለም ፡ ይገድፍ ፡ እግዚአብሔር ።
ወኢይደግምኑ ፡ እንከ ፡ ተሣህሎ ።
፰ ወቦኑ ፡ ለግሙራ ፡ ይመትር ፡ ምሕረቶ ፡ ለትውልደ ፡ ትውልድ ።
፱ ወይረስዕኑ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተሣህሎ ።
ወይደፍኑኑ ፡ ምሕረቶ ፡ በመዓቱ ።
፲ ወእቤ ፡ እምይእዜ ፡ ወጠንኩ ።
ከመ ፡ ዘያስተባርሮ ፡ የማኖ ፡ ልዑል ።
፲፩ ወተዘከርኩ ፡ ግብሮ ፡ ለእግዚአብሔር ።
እስመ ፡ እዜክር ፡ ዘትካት ፡ ምሕረተከ ።



እኔ ፡ ግን ፡ ለዘላለም ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፡ ፱
ለያዕቆብም ፡ አምላክ ፡ ዝማሬን ፡ አቀርባለሁና ።
የኃጥአንን ፡ ቀንዶች ፡ ሁሉ ፡ እሰብራለሁ ፡ ፲
የጻድቃን ፡ ቀንዶች ፡ ግን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላሉ ።

መዝሙር ፡ ፸፭ ።

ስለሕዝቅያስ ።

እግዚአብሔር ፡ በይሁዳ ፡ ታወቀ ፡ ፩
ስሙም ፡ በእስራኤል ፡ ታላቅ ፡ ነው ።
ስፍራው ፡ በሳሌም ፡ ማደሪያውም ፡ በጽዮን ፡ ነው ፡ ፪
በዚያም ፡ የቀስትን ፡ ኃይል ፡ ፫
ጋሻንና ፡ ሰይፍን ፡ ሰልፍንም ፡
ቀንዶችንም ፡ ሁሉ ፡ ሰባበረ ።
አንተ ፡ በዘላለም ፡ ተራሮች ፡ ሆነህ ፡ በድንቅ ፡ ታበራለህ ፡ ፬
ልበ ፡ ሰነፎች ፡ ሁሉ ፡ ደነገጡ ፡ ፭
እንቅልፋቸውንም ፡ አንቀላፉ ፡
ባለጠጎች ፡ ሁሉ ፡ በእነርሱ ፡ እጅ ፡ ምንም ፡ አላገኙም ።
የያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ ከተግሣጽህ ፡ የተነሣ ፡ ፮
ፈረሰኞች ፡ ሁሉ ፡ አንቀላፉ ።
አንተ ፡ ግን ፡ አንተ ፡ ግሩም ፡ ነህ ፡ ፯
ቍጣህን ፡ ማን ፡ ይቃወማል ። ?
ፍርድን ፡ ከሰማይ ፡ አሰማህ ፡ ፰
ምድር ፡ ፈራች ፡ ዝምም ፡ አለች ።
ልበ ፡ የዋሀን ፡ ያድን ፡ ዘንድ ፡ ፱
እግዚአብሔር ፡ ለፍርድ ፡ በተነሣ ፡ ጊዜ ።
ሰው ፡ በፈቃዱ ፡ ያመሰግንሃልና ፡ ፲
ከሕሊናቸው ፡ ትርፍም ፡ በዓልህን ፡ ያደርጋሉ ።
ለአምላካችን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስእለትን ፡ ክፈሉ ፤ ፲፩
በዙሪያው ፡ ያሉ ፡ ሁሉ ፡ እጅ ፡ መንሻን ፡ ለሚያስፈራው ፡ ያገባሉ ።
የመኳንንትን ፡ ነፍስ ፡ ያወጣል ፡ ፲፪
በምድርም ፡ ነገሥታት ፡ ዘንድ ፡ ያስፈራል ።

መዝሙር ፡ ፸፮ ።

ተግሣጽና ፡ ምክር ፡ ለሁሉ ።

በቃሌ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኽሁ ፡ ፩
ቃሌም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ደረሰ ፡ እርሱም ፡ አደመጠኝ
በመከራዬ ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፈለግሁት ፡ ፪
እጆቼ ፡ በሌሊት ፡ በፊቱ ፡ ናቸው ፡ አላረፍሁምም ፡
ነፍሴም ፡ መጽናናት ፡ አልተቻላትም ።
እግዚአብሔርን ፡ አሰብሁት ፡ ደስ ፡ አለኝም ፡ ፫
ተናገርሁ ፡ ነፍሴም ፡ ፈዘዘች ።
ዓይኖቼ ፡ እንዲተጉ ፡ አዘዝኻቸው ፡ ፬
ደነገጥሁ ፡ አልተናገርሁም ።
የዱሮውን ፡ ዘመን ፡ አሰብሁ ፡ ፭
የዘላለሙን ፡ ዓመታት ፡ አሰብሁ ፤ አጠናጠንሁም ።
በሌሊት ፡ ከልቤ ፡ ጋር ፡ ተጫወትሁ ፡ ፮
ነፍሴንም ፡ አነቃቃኋት ።
እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ ይጥላልን ? ፯
እንግዲህስ ፡ ቸርነቱን ፡ አይደግምምን ፡ ?
ለዘላለምስ ፡ ምሕረቱ ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ተቆረጠችን ፡ ፰
የተናገረውስ ፡ ቃል ፡ አልቆአልን ?
እግዚአብሔር ምገሱን ፡ ረሳን ? ፱
በቍጣውስ ፡ ምሕረቱን ፡ ዘጋውን ?
ይህ ፡ ድካሜ ፡ ነው ፡ አልሁ ፡ ፲
የልዑል ፡ ቀኝ ፡ እንደ ፡ ተለወጠ ።
የእግዚአብሔርን ፡ ሥራ ፡ አስታወስሁ ፡ ፲፩
የቀደመውን ፡ ተአምራትህን ፡ አስታውሳለሁና ።

፲፪ ወአነብብ ፡ በኵሉ ፡ ምግባሪከ ።
ወእዛዋዕ ፡ በግብርከ ።
፲፫ እግዚኦ ፡ ውስተ ፡ መቅደስ ፡ ፍኖትከ ።
መኑ ፡ አምላክ ፡ ዐቢይ ፡ ከመ ፡ አምላክነ ።
፲፬ አንተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ባሕቲትከ ፡ ዘትገብር፡መንክረ
አርአይኮሙ ፡ ለሕዝብከ ፡ ኀይለከ ።
ወአድኀንኮሙ ፡ ለሕዝብከ ፡ በመዝራዕትከ ።
፲፭ ለደቂቀ ፡ ያዕቆብ ፡ ወዮሴፍ ።
፲፮ ርእዩከ ፡ ማያት ፡ እግዚኦ ።
ርእዩከ ፡ ማያት ፡ ወፈርሁ ።
ደንገጹ ፡ ቀላያተ ፡ ማያት ፡ ወደምፀ ፡ ማያቲሆሙ ።
፲፯ ቃለ ፡ ወሀቡ ፡ ደመናት ፡ አሕጻከ ፡ ይወፅኡ ።
፲፰ ቃለ ፡ ነጐድጓድከ ፡ በሠረገላት ።
አስተርአየ ፡ መባርቅቲሁ ፡ ለዓለም ።
ርዕደት ፡ ወአድለቅለቀት ፡ ምድር ።
፲፱ ውስተ ፡ ባሕር ፡ ፍኖትከ ።
ወአሠርከኒ ፡ ውስተ ፡ ማይ ፡ ብዙኅ ።
ወኢይትዐወቅ ፡ አሠርከ ።
ወመራሕኮሙ ፡ ከመ ፡ አባግዕ ፡ ለሕዝብከ ።
፳ በእደ ፡ ሙሴ ፡ ወአሮን ።

መዝሙር ፡ ፸፯ ።
ተግሣጽ ፡ ለዘሉ ።

፩ አጽምዑ ፡ ሕዝብየ ፡ ሕግየ ።
ወጽልዉ ፡ እዝነክሙ ፡ ኀበ ፡ ቃለ ፡ አፉየ ።
፪ እከሥት ፡ በምሳሌ ፡ አፉየ ።
ወእነግር ፡ አምሳለ ፡ ዘእምትካት ።
፫ ኵሎ ፡ ዘሰማዕነ ፡ ወዘርኢነ ።
ወዘነገሩነ ፡ አበዊነ ።
ወኢኀብኡ ፡ እምደቂቆሙ ፡ ለካልእ ፡ ትውልድ ።
፬ ወነገሩ ፡ ስብሐቲሁ ፡ ለእግዚአብሔር ።
ኃይሎሂ ፡ ወመንክሮሂ ፡ ዘገብረ ።
ዘአቀመ ፡ ስምዐ ፡ ለያዕቆብ ።
ወሠርዐ ፡ ሕገ ፡ ለእስራኤል ።
ዘአዘዞሙ ፡ ለአበዊነ ።
፭ ከመ ፡ ይንግሩ ፡ ለደቂቆሙ ።
፮ ወከመ ፡ ያእምር ፡ ካልእ ፡ ትውልድ ።
ደቂቅ ፡ እለ ፡ ይትወለዱ ፡ ወይትነሥኡ ።
ወይዜንዉ ፡ ለደቂቆሙ ።
፯ ከመ ፡ ይረስዩ ፡ ትውክልቶሙ ፡ ላዕለ ፡ እግዚአብሔር ፡
ወከመ ፡ ኢይርስዑ ፡ ግብረ ፡ እግዚአብሔር ።
ወይኅሥሡ ፡ ትእዛዞ ።
ከመ ፡ ኢይኩኑ ፡ ከመ ፡ አበዊሆሙ ።
፰ ትውልድ ፡ ዕሉት ፡ ወመራር ።
ትውልድ ፡ እንተ ፡ ኢያርትዐት ፡ ልባ ።
ወኢተአመነት ፡ መንፈሳ ፡ በእግዚአብሔር ።
፱ ደቂቀ ፡ ኤፍሬም ፡ ይዌስቁ ፡ ወይነድፉ ።
ወተገፍትኡ ፡ እመ ፡ ዕለተ ፡ ቀትል ።
፲ እስመ ፡ ኢዐቀቡ ፡ ኪዳኖ ፡ ለእግዚአብሔር ።
ወአበዩ ፡ ሐዊረ ፡ በሕጉ ።
፲፩ ወረስዑ ፡ ረድኤቶ ።
ወመንክሮሂ ፡ ዘአርአዮሙ ።
ዘገብረ ፡ መንክረ ፡ በቅድመ ፡ አበዊሆሙ ።
፲፪ በምድረ ፡ ግብጽ ፡ ወበሐቅለ ፡ ጣኔዎስ ።
፲፫ ሠጠቀ ፡ ባሕረ ፡ ወአኅለፎሙ ።
ወዐቀመ ፡ ማየ ፡ ከመ ፡ ዝቅ ።
፲፬ መርሖሙ ፡ መዓልተ ፡ በደመና ።
ወኵሎ ፡ ሌሊተ ፡ በብርሃነ ፡ እሳት ።



በምግባርህም ፡ ሁሉ ፡ እናገራለሁ ፡ ፲፪
በሥራህም ፡ አወሳለሁ ።
አቤቱ ፡ መንገድህ ፡ በመቅደስ ፡ ውስጥ፡ ነው ፡ ፲፫
እንደ፡ አምላካችን ፡ ያለ ፡ ታላቅ ፡ አምላክ ፡ ማን፡ ነው ?
ተአምራትን ፡ የምታደርግ ፡ አምላክ ፡ አንተ ፡ ነህ ፡ ፲፬
ለሕዝብህ ፡ ኃይልህን ፡ አስታወቅሃቸው ።
የያዕቆብንና ፡ የዮሴፍን ፡ ልጆች ፡ ፲፭
ሕዝብህን ፡ በክንድህ ፡ አዳንሃቸው ።
አቤቱ ፡ ውኆች ፡ አዩህ ፡ ፲፮
ውኆችም ፡ አይተውህ ፡ ፈሩ ፡
ጥልቆች ፡ ተነዋወጡ ፡ ውኆችም ፡ ጮኹ ።
ደመናዎች ፡ ድምፅን ፡ ሰጡ ፡ ፲፯
ፍላጾችህም ፡ ወጡ ።
የነጐድጓድህ ፡ ድምፅ ፡ በዐውሎ ፡ ነበረ ፡ ፲፰
መብረቆች ፡ ለዓለም ፡ አበሩ ፡
ምድር ፡ ተናወጠች ፡ ተንቀጠቀጠችም ።
መንገድህ ፡ በባሕር ፡ መካከል ፡ ነው ፡ ፲፱
ፍለጋህም ፡ በብዙ ፡ ውኆች ፡ ውስጥ ፡ ነው ።
አረማመድህም ፡ አልታወቀም ።
በሙሴና ፡ በአሮን ፡ እጅ ፡ ፳
ሕዝብህን ፡ እንደ ፡ በጎች ፡ መራሃቸው ።

መዝሙር ፡ ፸፯ ።
ተግሣፅና ፡ ምክር ፡ ለሁሉ ።

ሕዝቤ ፡ ሆይ ፡ ሕጌን ፡ አድምጡ ፡ ፩
ጆሮአችሁንም ፡ ወደ፡አፌ ፡ ቃል ፡ አዘንብሉ ።
አፌን ፡ በምሳሌ ፡ እከፍታለሁ ፡ ፪
ከቀድሞ፡ ጀምሮ፡ ያለውንም፡ ተምሳሊት፡ እናገራለሁ ።
የሰማነውንና ፡ ያየነውን ፡ ፫
አባቶቻችንም ፡ የነገሩንን ፡
ለሚመጣው ፡ ትውልድ ፡ ከልጆቻቸው ፡ አንሰውርም ።
የእግዚአብሔርን ፡ ምስጋናና ፡ ኃይሉን ፡ ፬
ያደረገውንም ፡ ተአምራት ፡ እንናገራለን ።
ለልጆቻቸው ፡ ያስታውቁ ፡ ዘንድ ! ፭
ለአባቶቻችን ፡ ያዘዘውን ፡ ምስክር ፡
በያዕቆብ ፡ አቆመ ፡
በእስራኤልም ፡ ሕግን ፡ ሠራ ።
የሚመጣው ፡ ትውልድ ፡ የሚወለዱም ፡ ልጆች ፡
ያውቁ ፡ ዘንድ ።
ተነሥተው ፡ ለልጆቻቸው ፡ ይነግራሉ ። ፮
ተስፋቸውን ፡ በእግዚአብሔር ፡ እንዲያደርጉ ፡ ፯
የእግዚአብሔርንም ፡ሥራ ፡ እንዳይረሱ ።
ትእዛዙንም ፡ እንዲጠብቁ ።
እንደ፡አባቶቻቸው፡ጠማማና፡የምታስመርር፡ትውልድ፡ ፰
ልቧን ፡ ያላቀናች ፡ ትውልድ ፡
ነፍሷ ፡ በእግዚአብሔር ዘንድ፡ያልታመነች፡እንዳይሆኑ።
የኤፍሬም ፡ ልጆች ፡ ለሰልፍ ፡ ታጥቀው ፡ ፱
ቀስትንም፡ወርውረው፡በሰልፍ፡ቀን፡ወደ፡ኋላ፡ተመለሱ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ኪዳን ፡ አልጠበቁም ፡ ፲
በሕጉም ፡ ለመመላለስ ፡ እንቢ ፡ አሉ ።
መልካም ፡ ሥራውንና ፡ ያሳያቸውንም ፡ ፲፩
ተአምራቱን ፡ ሁሉ ፡ ረሱ ።
በግብጽ ፡ አገርና ፡ በጣኔዎስ ፡ በረሃ ፡ ፲፪
በአባቶቻቸው፡ ፊት፡ የሠራውን፡ ተአምራት ፡ ዘነጉ ።
ባሕርን ፡ ከፍሎ ፡ አሳለፋቸው ፡ ፲፫
ውኆችን ፡ እንደ ፡ ክምር ፡ አቆመ ።
ቀን ፡ በደመና ፡ ሌሊቱንም ፡ ሁሉ ፡ ፲፬
በእሳት ፡ ብርሃን ፡ መራቸው ፡

፲፭ ወአንቀዐ ፡ ኰኵሐ ፡ በበድው ።
ወአስተየሙ ፡ ከመ ፡ ዘእምቀላይ ፡ ብዙኅ ።
ወአውኀዘ ፡ ማየ ፡ ከመ ፡ ዘእምአፍላግ ።
፲፮ ወአውዕአ ፡ ማየ ፡ እምዕብን ።
፲፯ ደገሙ ፡ ዓዲ ፡ አብሶ ፡ ሎቱ ።
ወአምረርዎ ፡ ለልዑል ፡ በበድው ።
ወአመከርዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በልቦሙ ።
፲፰ ከመ ፡ ይስአሉ ፡ መብልዐ ፡ ለነፍሶሙ ።
፲፱ ሐመይዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ወይቤሉ ።
ይክልኑ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሠሪዐ ፡ ማእድ ፡ በገዳም ።
፳ ይዝብጥ ፡ ኰኵሐ ፡ ወያውኅዝ ፡ ማየ ።
ወይክልኑ ፡ ውሂበ ፡ ኅብስት ።
ወይሥራዕ ፡ ማእደ ፡ ለሕዝቡ ።
፳፩ ወሰምዐ ፡ ዘንተ ፡ እግዚአብሔር ወአናሕሰየ ።
ወነደ ፡ እሳት ፡ ላዕለ ፡ ያዕቆብ ።
ወመጽአ ፡ መቅሠፍት ፡ ላዕለ ፡ እስራኤል ።
፳፪ እስመ ፡ ኢተአመንዎ ፡ ለእግዚአብሔር ።
ወኢተወከሉ ፡ በአድኅኖቱ ።
፳፫ ወአዘዘ ፡ ደመና ፡ በላዕሉ ።
ወአርኃወ ፡ ኆኀተ ፡ ሰማይ ።
፳፬ ወአዝነመ ፡ ሎሙ ፡ መና ፡ ይብልዑ ።
ወወሀቦሙ ፡ ኅብስተ ፡ ሰማይ ።
፳፭ ወኅብስተ ፡ መላእክቲሁ ፡ በልዑ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ።
ፈነወ ፡ሎሙ ፡ ሥንቆሙ ፡ ዘየአክሎሙ ።
፳፮ ወአንሥአ ፡ አዜበ ፡ እምሰማይ ።
ወአምጽአ ፡ መስዐ ፡ በኀይሉ ።
፳፯ ወአዝነመ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ ሥጋ ፡ ከመ ፡ መሬት ።
ወከመ ፡ ኆፃ ፡ ባሕር ፡ አዕዋፈ ፡ዘይሰርር ።
፳፰ ወድቀ ፡ ማእከለ ፡ ተዓይኒሆሙ ።
ወዐውደ ፡ ደባትሪሆሙ ።
፳፱ በልዑ ፡ ወጸግቡ ፡ ጥቀ ።
ወወሀቦሙ ፡ ለፍትወቶሙ ።
፴ ወኢያኅጥአሙ ፡ እምዘፈቀዱ ።
ወእንዘ ፡ ዓዲ ፡ መብልዮሙ ፡ ውስተ ፡ አፉሆሙ ።
፴፩ ወመጽአ ፡ መቅሠፍተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ላዕሌሆሙ ።
ወቀተሎሙ ፡ መብዝኅቶሙ ።
ወአዕቀፆሙ ፡ ለኅሩያነ ፡ እስራኤል ።
፴፪ ወምስለ ፡ ዝኒ ፡ ዓዲ ፡ አበሱ ፡ ሎቱ ።
ወኢተአመንዎ ፡ በተአምሪሁ ።
፴፫ ወኀልቀ ፡ በከንቱ ፡ መዋዕሊሆሙ ።
ወኀለፈ ፡ በጕጕዓ ፡ ዓመቲሆሙ ።
፴፬ አመ ፡ ይቀትሎሙ ፡ ውእተ ፡ አሚረ ፡ የኀሥሥዎ ።
ይትመየጡ ፡ ወይገይሡ ፡ ኀበ ፡ እግዚአብሔር ።
፴፭ ወተዘከሩ ፡ ከመ፡እግዚአብሔር ውእቱ፡ረዳኢሆሙ ።
ወእግዚአብሔር ፡ ልዑል ፡ መድኅኒሆሙ ።
፴፮ ወአፍቀርዎ ፡ በአፉሆሙ ።
ወሐሰውዎ ፡ በልሳኖሙ ።
፴፯ ወኢኮነ ፡ ርቱዐ ፡ ልቦሙ ፡ በላዕሌሆሙ ።
ወኢተአመንዎ ፡ በኪዳኑ ።
፴፰ ውእቱሰ ፡ መሓሪ ፡ ውእቱ ።
ወይሰሪ ፡ ሎሙ፡ኵሎ፡ኀጢአቶሙ፡ወኢያጠፍአሙ ።
ወያበዝኅ ፡ መዩጠ ፡ መዓቶ ።
ወኢያነድድ ፡ በኵሉ ፡ መቅሠፍቶ ።
ወተዘከረ ፡ ከመ ፡ ሥጋ ፡ እሙንቱ
፴፱ መንፈስ ፡ እምከመ ፡ ወፅአ ፡ ኢይገብእ ።
ሚ ፡ መጠን ፡ አምዕዕዎ ፡ በገዳም ።
፵ ወወሐክዎ ፡ በበድው ።



ዓለቱን ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ሰነጠቀ ፤ ፲፭
ከጥልቅ፡ምንጭ፡እንደሚገኝ፡ውሀ፡በብዙ፡አጠጣቸው
ውኃን ፡ ከጭንጫ ፡ አፈለቀ ፤ ፲፮
ውኃንም ፡ እንደ ፡ ወንዞች ፡ አፈሰሰ ።
ነገር ፡ ግን ፡ ይበድሉት ፡ዘንድ፡እንደ ፡ገና፡ደገሙ ፤ ፲፯
ልዑልንም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ አስቆጡት ።
ለነፍሳቸው ፡ መብልን ፡ ይፈልጉ ፡ ዘንድ ፤ ፲፰
እግዚአብሔርን ፤ በልባቸው ፡ ፈተኑት ።
እግዚአብሔርን ፤ እንዲህ ፡ ብለው ፡ አሙት ፤ ፲፱
እግዚአብሔር ፤ በምድረ፡ በዳ፡ ማዕድን፡ ያሰናዳ ፤
ዘንድ ፡ ይችላልን ? አሉ ።
ዓለቱን፡ መታ፤ ውኆችም፡ ወጡ ፤ ጐርፎችም፡ ጐረፉ ፤ ፳
እንደገናም ፡ እንጀራን ፡ መስጠትስ ፡ ይችላልን ?
ለሕዝቡስ ፡ ማዕድን ፡ ያዘጋጅልን ፡ አሉ ?
እግዚአብሔርም ፡ ይህን ፡ ሰምቶ ፡ ተቆጣ ፤ ፳፩
በያዕቆብም ፡ ላይ ፡ እሳት ፡ ነደደ ፤
መዓትም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ወረደ ፤
በእግዚአብሔር ፤ አላመኑምና ፤ ፳፪
በመድኃኒቱም ፡ አልተማመኑምና ።
ደመናውንም ፡ ከላይ ፡ አዘዘ ፤ ፳፫
የሰማይንም ፡ ደጆች ፡ ከፈተ ።
ይበሉም ፡ ዘንድ ፡ መናን ፡ አዘነመላቸው ፤ ፳፬
የሰማይንም ፡ እንጀራ ፡ ሰጣቸው ።
የመላእክትንም ፡ እንጀራ ፡ ሰው ፡ በላ ፤ ፳፭
ስንቅንም ፡ እስኪጠግቡ ፡ ላከላቸው ።
ከሰማይ ፡ የምሥራቅን ፡ ነፋስ ፡ አስነሣ ፤ ፳፮
በኃይሉም ፡ የደቡብን ፡ ነፋስ ፡ አመጣ ።
ሥጋን ፡ እንደ ፡ አፈር ፤ ፳፯
የሚበሩትንም፡ወፎች፡እንደባሕር፡አሸዋ፡አዘነመላቸው፤
በሰፈራቸው ፡ መካከል ፤ ፳፰
በድንኳናቸውም ፡ ዙሪያ ፡ ወደቀላቸው ።
በሉ ፡ እጅግም ፡ ጠገቡ ፤ ፳፱
ምኞታቸውንም ፡ ሁሉ ፡ ሰጣቸው ።
ከወደዱትም ፡ አላሳጣቸውም ፤ ፴
መብላቸውም ፡ ገና ፡ በአፋቸው ፡ ሳለ ፤
የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ በላያቸው ፡ መጣ ፤ ፴፩
ከእነርሱም ፡ ብዙት ፡ ያላቸውን ፡ ገደለ ፤
የእስራኤልንም ፡ ምርጦች ፡ አሰናከለ ።
ከዚህም ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ እንደ ፡ ገና ፡ በደሉ ፤ ፴፪
ተአምራቱንም ፡ አላመኑም ፤
ቀኖቻቸውም ፡ በከንቱ ፡ አለቁ ፤ ፴፫
ዓመቶቻቸውም ፡ በችኰላ ፡ አለፉ ።
በገደላቸውም ፡ ጊዜ ፡ ወዲያው ፡ ፈለጉት ፤ ፴፬
ተመለሱ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ገሠገሡ ።
ረዳታቸውም ፡ እግዚአብሔር ፤ ፴፭
መድኃኒታቸውም፤ ልዑል፡ አምላክ፡ እንደሆነ፡ አሰቡ
በአፋቸው ፡ ብቻ ፡ ወደዱት ፤ ፴፮
በአንደበታቸው ፡ ግን ፡ ዋሹበት ፤
ልባቸውም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ አልቀናም ፤ ፴፯
በቃል ፡ ኪዳኑም ፡ አልተማመኑም ።
እርሱ ፡ ግን ፡ መሓሪ ፡ ነው ፤ ፴፰
ኃጢአታቸውንም፡ ይቅር፡አላቸው፡አላጠፋቸውምም ።
ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ቍጣውን ፡ ከነሱ ፡ መለሰ ፤
መዓቱንም ፡ አላመጣባቸውም ።
ወጥቶ ፡ የማይመለስ ፡ መንፈስ ፤ ፴፱
ሥጋም ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ አሰበ ።
በምድረ ፡ በዳ፡ ምን፡ ያህል ፡ አስቆጡት ፤ ፵
በበረሃም ፡ አሳዘኑት ።

፵፩ ተመይጡ ፡ ወአመከርዎ ፡ ለእግዚአብሔር ።
ወወሀክዎ ፡ ለቅዱስ ፡ እስራኤል ።
፵፪ ወኢተዘከሩ ፡ እዴሁ ።
ዘአድኃኖሙ ፡ እምእደ ፡ ፀሮሙ ።
፵፫ ዘገብረ ፡ ተአምረ ፡ በግብጽ ።
ወመንክረ ፡ በሐቅለ ፡ ጣኔዎስ ።
፵፬ ወረሰየ ፡ ደመ ፡ ለአፍላጊሆሙ ።
ወለአንቅዕቲሆሙኒ ፡ ከመ ፡ ኢይስተይዎ ።
፵፭ ፈነወ ፡ ሳዕሊሆሙ ፡ ዐኰተ ፡ ወበልዖሙ ።
ወቈርናናዓተ ፡ ወአርኰሶሙ ።
፵፮ ወወሀበ ፡ ለአናኵዕ ፡ ፍሬሆሙ ።
ወተግባሮሙኒ ፡ ለአንበጣ ።
፵፯ ወቀተለ ፡ ወይኖሙ ፡ በበረድ ።
ወበለሶሙኒ ፡ በአስሐትያ ።
፵፰ ወወሀበ ፡ ለበረድ ፡ እንስሳሆሙ ።
ወንዋዮሙኒ ፡ ለእሳት ።
፵፱ ፈነወ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ መቅሠፍተ ፡ መዓቱ ።
መቅሠፍተ ፡ ወመንሱተ ፡ ወሕማመ ።
ወፈነወ ፡ ምስለ ፡ መላእክት ፡ እኩያን ።
፶ ወጼሐ ፡ ፍኖተ ፡ ለመዓቱ ።
ወኢምሀከ ፡ እሞት ፡ ለነፍሶሙ ።
ወዐጸወ ፡ ውስተ ፡ ሞት ፡ እንስሳሆሙ ።
፶፩ ወቀተለ ፡ ኵሎ ፡ በኵሮሙ ፡ በምድረ ፡ ግብፅ ።
ወቀዳሚ ፡ ኵሉ ፡ ፃማሆሙ ፡ በውስተ ፡ አብያቲሆሙ ።
፶፪ ወአውፈሮሙ ፡ ከመ ፡ አባግዕ ፡ ለሕዝቡ ።
ወአውዕኦሙ ፡ ገዳመ ፡ ከመ ፡ መርዔት ።
፶፫ ወመርሆሙ ፡ በተስፋሁ ፡ ወኢፈርሁ ።
ወደፈኖሙ ፡ ባሕር ፡ ለፀሮሙ ።
፶፬ ወወሰዶሙ ፡ ደብረ ፡ መቅደሱ ።
ደብር ፡ ዘፈጠረት ፡ የማኑ ።

፶፭ ሰደደ ፡ አሕዛበ ፡ እምቅድመ ፡ ገጾሙ ።
ወአውረሶሙ ፡ በሐብለ ፡ ርስቱ ።
ወአንበረ ፡ ውስተ ፡ አብያቲሆሙ ፡ ሕዝበ ፡ እስራኤል ።
፶፮ አመከርዎ ፡ ወአምዕዕዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ልዑል ።
ወኢዐቀቡ ፡ ስምዖ ።
፶፯ ተመይጡ ፡ ወዐለዉ ፡ ከመ ፡ አበዊሆሙ ።
ወኮኑ ፡ ከመ ፡ ቀስት ፡ ጠዋይ ።
፶፰ ወአምዕዕዎ ፡ በአውግሪሆሙ ።
ወአቅንዕዎ ፡ በግልፎሆሙ ።
፶፱ ወሰምዐ ፡ ዘንተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወአናሕሰየ ።
ወመነኖሙ ፡ ለእስራኤል ፡ ፈድፋደ ።
፷ ወኀደጋ ፡ ለደብተራ ፡ ሴሎም ።
ደብተራሁ ፡ እንተ ፡ ባቲ ፡ ኀደረ ፡ ምስለ ፡ ሰብእ ።
፷፩ ወወሀበ ፡ ኀይሎሙ ፡ ለተጼውዎ ።
ወሥነሙኒ ፡ ውስተ ፡ እደ ፡ ፀሮሙ ።
፷፪ ወአጸምሙ ፡ ውስተ ፡ ኲናት ፡ ለሕዝቡ ።
ወተሀየዮሙ ፡ ለርስቱ ።
፷፫ ወበልዐቶሙ ፡ እሳት ፡ ለወራዙቶሙ ።
ወኢለሐዋ ፡ ደናግሊሆሙ ።
፷፬ ወካህናቲሆሙኒ ፡ ወድቁ ፡ በኲናት ።
ወኢበከያ ፡ ዕቤራቲሆሙ ።
፷፭ ወተንሥአ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከመ፡ዘንቃህ፡እምንዋም።
ወከመ ፡ ኃያል ፡ ወኅዳገ ፡ ወይን ።
፷፮ ወቀተለ ፡ ፀሮ ፡ በድኅሬሁ ።
ወወሀቦሙ ፡ ኀሳረ ፡ ዘለዓለም ።
፷፯ ወኀደጋ ፡ ለደብተራ ፡ ዮሴፍ ።
ወኢኀረየ ፡ ለሕዝበ ፡ ኤፍሬም ።
፷፰ ወኀረየ ፡ ለሕዝበ ፡ ይሁዳ ።
ደብረ ፡ ጽዮን ፡ ዘአፍቀረ ።



ተመለሱ ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ፈተኑት ፡ ፵፩
የእስራኤልንም ፡ ቅዱስ ፡ አሳዘኑት ።
እነርሱም ፡ እጁን ፡ አላሰቡም ፡ ፵፪
ከጠላቶቻቸው ፡ እጅ ፡ ያዳነበትን ፡ ቀን ፡
በግብጽ ፡ ያደረገውን ፡ ተአምራቱን ፡ ፵፫
በጣኔዎስም፡ በረሃ፡ ያደረገውን፡ ድንቁን፡ ረስተዋልና ።
ወንዞቻቸውንም ፡ ወደ ፡ ደም ፡ ለወጠ ፡ ፵፬
ምንጮቻቸውን ፡ ደግሞ ፡ እንዳይጠጡ ።
ዝንቦችንም፡በላያቸው፡ ሰደደባቸው፡ በሉአቸውም ፡ ፵፭
በጓጉንቸርም ፡ አጠፋቸው ።
ፍሬያቸውን ፡ ለኩብኩባ ፡ ፵፮
ሥራቸውንም ፡ ለአንበጣ ፡ ሰጠ ።
ወይናቸውን ፡ በበረዶ ፡ ፵፯
በለሳቸውንም ፡ በአመዳይ ፡ አጠፋ ።
እንስሶቻቸውን ፡ ለበረዶ ፡ ፵፰
ሀብታቸውንም ፡ ለእሳት ፡ ሰጠ ።
የመዓቱን ፡ መቅሠፍት ፡ በላያቸው ፡ ሰደደ ፡ ፵፱
መቅሠፍትን ፡ መዓትንም ፡ መከራንም ፡
ከክፉዎች ፡ መላእክት ፡ ጋር ፡ ሰደደ ።
ለቍጣው ፡ መንገድን ፡ ጠረገ ፡ ፶
ነፍሳቸውንም ፡ ከሞት ፡ አላዳናትም ።
እንስሶቻቸውንም ፡ በሞት ፡ ውስጥ ፡ ዘጋ ።
በኵሮቻቸውን ፡ ሁሉ ፡ በግብፅ ፡ ፶፩
የድካማቸውንም ፡ መጀመሪያ ፡ በካም ፡ ድንኳኖች ፡ ገደለ ።
ሕዝቡን ፡ ግን ፡ እንደ ፡ በጎች ፡ አሰማራቸው ፡ ፶፪
እንደ ፡ መንጋም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ መራቸው ።
በተስፋም ፡ መራቸው ፡ አልፈሩም ፡ ፶፫
ጠላቶቻቸውንም ፡ ባሕር ፡ ደፈናቸው ።
ወደ ፡ መቅደሱም ፡ ተራራ ፡ አገባቸው ፡ ፶፬
ቀኙ ፡ ወደ ፡ ፈጠረችው ፡ ወደዚችም ፡ ተራራ ።

ከፊታቸውም ፡ አሕዛብን ፡ አባረረ ፡ ፶፭
ርስቱንም ፡ በገመድ ፡ አካፈላቸው ፡
የእስራኤልንም ፡ ወገኖች ፡ በቤታቸው ፡ አኖረ ።
ነገር ፡ ግን ልዑል ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፈተኑት ፡ ፶፮
አስቆጡትም ፡ ምስክርነቱንም ፡ አልጠበቁም ።
ተመለሱም ፡ እንደ ፡ አባቶቻቸውም ፡ ከዱ ፡ ፶፯
እንደ ፡ ጠማማ ፡ ቀስትም ፡ ተገለበጡ ።
በኮረብቶቻቸውም ፡ አስቈጡት ፡ ፶፰
በጣዖቶቻቸውም ፡ አስቀኑት ።
እግዚአብሔርም ፡ ይህን ፡ ሰምቶ ፡ ተቈጣ ፡
እስራኤልንም ፡ እጅግ ፡ ናቀ ።
የሴሎምን ፡ ድንኳን ፡ ተዋት ፡ ፷
በሰዎች ፡ መካከል ፡ ያደረገባትንም ፡ ድንኳኑን ።
ኃይላቸውን ፡ ለምርኮ ፡ ፷፩
ሽልማቱን ፡ በጠላት ፡ እጅ ፡ ሰጠ ።
ሕዝቡንም ፡ በጦር ፡ ውስጥ ፡ ዘጋቸው ፡ ፷፪
ርስቱንም ፡ ቸል ፡ አላቸው ።
ጐልማሶቻቸውን ፡ እሳት ፡ በላቸው ፡ ፷፫
ቈነጃጅቶቻቸውም ፡ አልተዋቡም ።
ካህናቶቻቸውም ፡ በሰይፍ ፡ ወደቁ ፡ ፷፬
ባልቴቶቻቸውም ፡ አላለቀሱላቸውም ።
እግዚአብሔርም ፡ ከእንቅልፍ፡እንደሚነቃ፡ተነሣ ፡ ፷፭
የወይን፡ስካር፡እንደ፡ተወው፡እንደ ፡ ኃይለኛም ፡ ሰው ።
ጠላቶቹንም ፡ በኋላቸው ፡ መታ ፡ ፷፮
የዘላለምን ፡ ኀሣር ፡ ሰጣቸው
የዮሴፍንም ፡ ድንኳን ፡ ተጣት ፡ ፷፯
የኤፍሬምንም ፡ ወገን ፡ አልመረጠውም ።
የይሁዳንም ፡ ወገን ፡ መረጠ ፡ ፷፰
የወደደውንም ፡ የጽዮንን ፡ ተራራ ።

፷፱ ሐነጸ ፡ መቅደሶ ፡ በአርያም ።
ወሣረራ ፡ ውስተ ፡ ምድር ፡ ዘለዓለም ።
፸ ወኀረዮ ፡ ለዳዊት ፡ ገብሩ ።
ወነሥኦ ፡ እመርዔተ ፡ አባግዒሁ ።
፸፩ ወተመጥዎ ፡ እምድኅረ ፡ ሐራሳት ።
ከመ ፡ ይርዐዮ ፡ ለያዕቆብ ፡ ገብሩ ።
ወለእስራኤል ፡ ርስቱ ።
፸፪ ወርዐዮሙ ፡ በየዋሃተ ፡ ልቡ ።
ወመርሐሙ ፡ በጥበበ ፡ እደዊሁ ።

መዝሙር ፡ ፸፰ ።

በእንተ መቃብያን ።

፩ እግዚኦ ፡ ቦኡ ፡ አሕዛብ ፡ ውስተ ፡ ርስትከ ።
ወአርኰሱ ፡ ጽርሐ ፡ መቅደስከ ።
ወረሰይዋ ፡ ለኢየሩሳሌም፡ከመ፡ልገተ፡ዐቃቤ፡ቀምሕ።
፪ ወረሰዩ አብድንቲሆሙ ለአግብርቲከ መብልዐ ለአዕዋፈ ሰማይ
ወሥጋሆሙኒ ፡ ለጻድቃኒከ ፡ ለአራዊተ ፡ ገዳም ።
፫ ወከዐዉ ፡ ደሞሙ ፡ ከመ፡ማይ፡ዐውዳ፡ለኢየሩሳሌም ።
ወኀጥኡ ፡ ዘይቀብሮሙ ።
፬ ወኮነ ፡ ጽዕለተ ፡ ለጎርን ።
ሠሐቀ ፡ ወሥላቀ ፡ ለአድያሚነ ።
፭ እስከ ፡ ማእዜኑ ፡ እግዚኦ ፡ ትትመዐዕ ፡ ለዝሉፉ ።
ወይነድድ ፡ ከመ ፡ እሳት ፡ ቅንዓትከ ።
ከዐው ፡ መዓተከ ፡ ላዕለ ፡ አሕዛብ ፡ እለ ፡ ኢየአምሩከ።
፮ ወላዕለ ፡ መንግሥት ፡ እንተ ፡ ኢጸውዐት ፡ ስመከ ።
፯ እስመ ፡ በልዕዎ ፡ ለያዕቆብ ፡ ወአማሰኑ ፡ ብሔሮ ።
፰ ኢትዝክር ፡ ለነ ፡ አበሳነ ፡ ዘትካት ።
ፍጡነ ፡ ይርከበነ ፡ ሣህልከ ፡ እግዚኦ ።
እስመ ፡ ተመንደብነ ፡ ፈድፋደ ።
፱ ርድአነ ፡ አምላክነ ፡ ወመድኃኒነ ።
በእንተ ፡ ስብሐተ ፡ ስምከ ፡ እግዚኦ ፡ ባልሐነ ።
ወሥረይ ፡ ለነ ፡ ኀጢአተነ ፡ በእንተ ፡ ስምከ ።
፲ ከመ ፡ ኢይበሉነ ፡ አሕዛብ፡አይቴ፡ውእቱ፡አምላኮሙ።
ወይርአዩ ፡ አሕዛብ ፡ በቅድመ ፡ አዕይንቲነ ።
በቀለ ፡ ደሞሙ ፡ ለአግብርቲከ ፡ ዘተክዕወ ።
፲፩ ይባእ ፡ ቅድሜከ ፡ ገዓሮሙ ፡ ለሙቁሓን ።
ወበከመ ፡ ዕበየ ፡ መዝራዕትከ ።
ተሣሀሎሙ ፡ ለደቂቀ ፡ ቅቱላን ።
ፍድዮሙ ፡ ለጎርን ፡ ምስብዒተ ፡ ውስተ ፡ ሕፅኖሙ ።
፲፪ ትዕይርቶሙ ፡ ዘተዓየሩከ ፡ እግዚኦ ።
፲፫ ንሕነሰ ፡ ሕዝብከ ፡ ወአባግዐ ፡ መርዔትከ ።
ወንገኒ ፡ ለከ ፡ ለዓለም ።
ወንነግር ፡ ስብሐቲከ ፡ ለትውልደ ፡ ትውልድ ።

መዝሙር ፡ ፸፱ ።

በእንተ መቃብያን ወበእንተ ትሩፋን ።

፩ ኖላዊሆሙ ፡ ለእስራኤል ፡ አጽምዕ ።
ዘይርዕዮሙ ፡ ከመ ፡ አባግዐ ፡ ዮሴፍ ።
ዘይነብር ፡ ላዕለ ፡ ኪሩቤል ፡ አስተርእየ ።
፪ በቅድመ ፡ ኤፍሬም ፡ ወብንያም ፡ ወምናሴ ።
አንሥእ ፡ ኀይለከ ፡ ወነዐ ፡ አድኅነነ ።
፫ አምላክ ፡ ኀያላን ፡ ሚጠነ ።
አብርህ ፡ ገጸከ ፡ ላዕሌነ ፡ ወንድኅን ።
፬ እግዚኦ ፡ አምላክ ፡ ኀያላን ።
እስከ ፡ ማእዜኑ ፡ ትትመዐዕ ፡ ላዕለ ፡ ጸሎተ ፡ ገብርከ ።
፭ ወትሴስየነ ፡ እክለ ፡ አንብዕነ ።
ወታሰትየነ ፡ አንብዐነ ፡ በመስፈርት ።
፮ ወረሰይከነ ፡ ነገረ ፡ ለጎርን ።
ወተሣለቁ ፡ ላዕሌነ ፡ ጸላእትነ ።



መቅደሱን ፡ እንደ ፡ አርያም ፡ ሠራ ፡ ፷፱
ለዘላለምም ፡ በምድር ፡ ውስጥ ፡ መሠረታት ።
ዳዊትንም ፡ ባሪያውን ፡ መረጠው ፡ ፸
ከበጎቹም ፡ መንጋ ፡ ውስጥ ፡ ወሰደው ።
ከሚያጠቡ ፡ በጎችም ፡ በኋላ ፡ ፸፩
ባሪያውን ፡ ያዕቆብን ።
ርስቱንም ፡ እስራኤልን ፡ ይጠብቅ ፡ ዘንድ ፡ ወሰደው ።
በልቡ ፡ ቅንነት ፡ ጠበቃቸው ፡ ፸፪
በእጁም ፡ ብልሃት ፡ መራቸው ።

መዝሙር ፡ ፸፰ ።

ስለ መቃብያን ።

አቤቱ ፡ አሕዛብ ፡ ወደ ፡ ርስትህ ፡ ገቡ ፡ ፩
የቅድስናህንም ፡ መቅደስ ፡ አረከሱ ።
ኢየሩሳሌምንም ፡ እንደ ፡ መደብ ፡ አደረጓት ።
የባሮችህንም፡በድኖች፡ለሰማይ፡ወፎች፡ መብል፡ አደረጉ ፪
የጻድቃንህንም ፡ ሥጋ ፡ ለምድር ፡ አራዊት ።
ደማቸውንም፡በኢየሩሳሌም፡ዙሪያ፡እንደ፡ውሃ፡አፈሰሱ ፡ ፫
የሚቀብራቸውም ፡ አጡ ።
ለጎረቤቶቻችንም ፡ ስድብ ፡ ሆንን ። ፬
በዙሪያችንም ፡ ላሉ ፡ ሣቅና ፡ ዘበት ።
አቤቱ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ለዘላለም ፡ ትቈጣለህ ? ፭
ቅንዓትህም ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ ይነዳል ?
ያዕቆብን ፡ በልተውታልና ፡ ፮
ስፍራውንም ፡ ባድማ ፡ አድርገዋልና ፡
ስምህን ፡ በማይጠሩ ፡ መንግሥታት ፡ ላይ ፡ ፯
በማያውቁህም ፡ አሕዛብ፡ላይ ፡ መዓትህን ፡ አፍስስ ።
የቀደመውን ፡ በደላችንን ፡ አታስብብን ፡ ፰
ምሕረትህ ፡ በቶሎ ፡ ታግኘን ፡
እጅግ ፡ ተቸግረናልና ።
አምላካችንና ፡ መድኃኒታችን ፡ ሆይ ፡ እርዳን ፡ ፱
ስለ ፡ስምህ ፡ ክብር ፡ አቤቱ ፡ ታደገን ፡
ስለ ፡ ስምህም ፡ ኃጢአታችንን፡ አስተሥርይልን ።
አሕዛብ ፡ አምላካቸው ፡ ወዴት፡ነው ? እንዳይሉ ፡ ፲
የፈሰሰውን ፡ የባሪያዎችህን ፡ ደም ፡ በቀል ፡
በዓይኖቻችን ፡ ፊት ፡ አሕዛብ ፡ ይወቁ ።
የእስረኞች ፡ ጩኸት ፡ ወደ ፡ ፊትህ ፡ ይግባ ፡ ፲፩
እንደ ፡ ክንድህም ፡ ታላቅነት ፡ ሊገደሉ ፡ የተፈረደ
ባቸውን ፡ አድን ።
አቤቱ ፡ የተዘባበቱብህን ፡ መዘባበታቸውን ፡ ፲፪
ለጎረቤቶቻችን፡ ሰባት፡እጥፍ፡ በብብታቸው፡ ክፈላቸው ።
እኛ ፡ ሕዝብህ ፡ ግን ፡ የመሰማሪያህም ፡ በጎች ፡ ፲፫
ለዘላለም ፡ እናመሰግንሃለን ፤
ለልጅ ፡ ልጅም ፡ ምስጋናህን ፡ እንናገራለን ።

መዝሙር ፡ ፸፱ ።

ስለ ፡ ትሩፋንና ስለ ፡ መቃብያን ።

ዮሴፍን ፡ እንደ ፡ መንጋ ፡ የምትመራ ፡ ፩
የእስራኤል ፡ ጠባቂ ፡ ሆይ ፡ አድምጥ ፤
በኪሩቤል ፡ ላይ ፡ የምትቀመጥ ፡ ተገለጥ ።
በኤፍሬምና ፡ በብንያም ፡ በምናሴም ፡ ፪
ኃይልህን ፡ አንሣ ፡ እኛንም ፡ ለማዳን ፡ ና ።
አቤቱ ፡ መልሰን ፡ ፫
ፊትህንም ፡ አብራ ፡ እኛም ፡ እንድናለን ።
የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ አቤቱ ፡ ፬
በባሪያህ ፡ ጸሎት ፡ ላይ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ትቆጣለህ ?
የእንባ ፡ እንጀራን ፡ ትመግበናለህ ፡ ፭
እንባም ፡ በስፍር ፡ ታጠጣናለህ ።
ለጎረቤቶቻችን ፡ ክርክር ፡ አደረግኸን ፡ ፮
ጠላቶቻችንም ፡ በላያችን ፡ ተሣለቁብን ።

፯ እግዚኦ ፡ አምላከ ፡ ኃያላን ፡ ሚጠነ ።
አብርህ ፡ ገጸከ ፡ ላዕሌነ ፡ ወንድኀን ።
፰ ዐጸደ ፡ ወይን ፡ አፍለስከ ፡ እምግብጽ ።
ሰደድከ ፡ አሕዛበ ፡ ወተከልከ ፡ ኪያሃ ።
፱ ወጼሕከ ፡ ፍኖተ ፡ ቅድሜሃ ።
ተከልከ ፡ ሥረዊሃ ፡ ወመልዓት ፡ ምድረ ።
፲ ወከደነ ፡ አድባረ ፡ ጽላሎታ ።
ወአዕጹቂሃኒ ፡ ከመ ፡ አርዘ ፡ እግዚአብሔር ።
፲፩ ወሰፍሐ ፡ አዕጹቂሃ ፡ እስከ ፡ ባሕር ።
ወእስከ ፡ አፍላግ ፡ ሠርጸ ።
፲፪ ለምንት ፡ ትነሥት ፡ ጸቈና ።
ወይበልዓ ፡ ኵሉ ፡ ኀላፌ ፡ ፍኖት ።
፲፫ ወአርኰሳ ፡ ሐራውያ ፡ ሐቅል ።
ወተርዕያ ፡ እንስሳ ፡ ገዳም ።
፲፬ አምላከ ፡ ኃያላን ፡ ተመየጥ ።
ሐውጽ ፡ እምሰማይ ፡ ወርኢ ።
ወተማሀላ ፡ ለዛ ፡ ዐፀደ ፡ ወይን ።
፲፭ አስተናሥኦ ፡ ወአጽንዓ ፡ ዘተከለት ፡ የማንከ ።
በወልደ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ፡ ዘአጽናእከ ፡ ለከ ።
፲፮ ለውዓት ፡ በእሳት ፡ ወምልኅት ።
እምተግሣጸ ፡ ገጽከ ፡ ይትሀጐሉ ።
ለይኩን ፡ እዴከ ፡ ላዕለ ፡ ብእሲ ፡ የማንከ ።
፲፯ በወልደ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ፡ ዘአጽናዕከ ፡ ለከ ።
፲፰ ወኢንርኃቅ ፡ እምኔከ ።
አሕይወነ ፡ ወንጸውዕ ፡ ስመከ ።
፲፱ እግዚኦ ፡ አምላከ ፡ ኃያላን ፡ ሚጠነ ።
አብርህ ፡ ገጸከ ፡ ላዕሌነ ፡ ወንድኀን ።

መዝሙር ፡ ፹ ።
በእንተ ትፍሥት ።

፩ ተፈሥሑ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘረድአነ ።
ወየብቡ ፡ ለአምላከ ፡ ያዕቆብ ።
፪ ንሥኡ ፡ መዝሙረ ፡ ወሀቡ ፡ ከበሮ ።
መዝሙር ፡ ኀዋዝ ፡ ዘመስለ ፡ መሰንቆ ።
፫ ንፍሑ ፡ ቀርነ ፡ በዕለተ ፡ ሠርቅ ።
በዕምርት ፡ ዕለት ፡ በዓልነ ።
፬ እስመ ፡ ሥርዐቱ ፡ ለእስራኤል ፡ ውእቱ ።
ወፍትሑ ፡ ለአምላከ ፡ ያዕቆብ ።
ዘአቀመ ፡ ስምዐ ፡ ለዮሴፍ ።
፭ አመ ፡ የሐውር ፡ ብሔረ ፡ ግብጽ ።
ወሰምዐ ፡ ልሳነ ፡ ዘኢየአምር ።
፮ ወሚጠ ፡ ዘባኖ ፡ እምሕራማቲሆሙ ።
ወተቀንየ ፡ እደዊሁ ፡ ውስተ ፡ አክፋር ።
፯ በምንዳቤከ ፡ ጸዋዕከኒ ፡ ወአድኀንኩከ ።
ወተሰጠውኩከ ፡ በዐውሎ ፡ ኀቡእ ።
ወአመከርኩከ ፡ በኀበ ፡ ማየ ፡ ቅሰት ።
፰ ስምዐኒ ፡ ሕዝብየ ፡ ወእንግርከ ።
እስራኤል ፡ አሰምዕ ፡ ለከ ።
፱ እመሰ ፡ ሰማዕከኒ ፡ ኢይከውነከ ፡ አምላከ ፡ግብት ።
ወኢትስግድ ፡ ለአምላከ ፡ ነኪር ።
እስመ ፡ አነ ፡ ውእቱ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክከ ።
፲ ዘአውፃእኩከ ፡ እምድረ ፡ ግብጽ ።
አርሕብ ፡ አፉከ ፡ ወእመልኦ ፡ ለከ ።
፲፩ ወኢሰምዑኒ ፡ ሕዝብየ ፡ ቃልየ ።
ወእስራኤልኒ ፡ ኢያጽምዑኒ ።
፲፪ ወፈነውኩ ፡ ሎሙ ፡ በከመ ፡ ምግባሮሙ ።
ወሖሩ ፡ በኀሊና ፡ ልቦሙ ።



የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ አቤቱ ፡ መልሰን ፡ ፯
ፊትህንም ፡ አብራ ፡ እኛም ፡ እንድናለን ።
ከግብጽ ፡ የወይን ፡ ግንድ፡ አመጣህ ፡ ፰
አሕዛብን ፡ አባረርህ ፡ እርስዋንም ፡ ተክልህ ።
በፊቷም ፡ ስፍራን ፡ አዘጋጀህ ፡ ፱
ሥሮቿንም ፡ ተክልህ፡ምድርንም፡መላች ።
ጥላዋ ፡ ተራሮችን ፡ ከደነ ፡ ፲
ጫፎቿም ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዝግባ ፡ ሆኑ ።
ቅርንጫፎችዋንም ፡ እስከ ፡ ባሕር ፡ ፲፩
ከንፎቿንም ፡ እስከ ፡ ወንዙ ፡ ዘረጋች ።
አጥሯን ፡ ለምን ፡ አፈረስህ ? ፲፪
መንገድ ፡ አላፊም ፡ ሁሉ ፡ ይቀጥፋታል ።
የዱር ፡ እሪያ ፡ አረከሳት ፡ ፲፫
የበረኃ ፡ አውሬም ፡ ተሰማራባት ።
የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ እንግዲህ ፡ ተመለስ ፡ ፲፬
ከሰማይ ፡ ተመልከት ፡ እይም ፡
ይህችንም ፡ የወይን ፡ ግንድ ፡ ጐብኝ ።
በሰው ፡ ልጅ ፡ ለአንተ ፡ ያጸናኸውን ፡ ፲፭
ቀኝህ ፡ የተከላትን ፡ አንጻ ።
ተንቅላለች ፡ በእሳትም ፡ ተቃጥላማለች ፡ ፲፮
ከፊትህ ፡ ተግሣጽም ፡ የተነሣ ፡ ይጠፋሉ ።
ለአንተ ፡ ባጸናኸው ፡ በሰው ፡ ልጅ ፡ ላይ ፡ ፲፯
በቀኝህም ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ እጅህ ፡ ትሁን ።
ከአንተም ፡ አንራቅ ፡ ፲፰
አድነን ፡ ስምህንም ፡ እንጠራለን ።
የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ አቤቱ ፡ መልሰን ፡ ፲፱
ፊትህንም ፡ አብራ ፡ እኛም ፡ እንድናለን ።

መዝሙር ፡ ፹ ።
ስለ ፡ ትፍሥት ።

በረድኤታችን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፡ ፩
ለያዕቆብም ፡ አምላክ ፡ እልል ፡ በሉ ።
ዝማሬውን ፡ አንሡ ፡ ከበሮንም ፡ አምጡ ፡ ፪
ደስ ፡ የሚያሰኘውን ፡ በገና ፡ ከመሰንቆ ፡ ጋር ፤
በመባቻ ፡ ቀን ፡ በከፍተኛው ፡ በዓላችን ፡ ቀን ፡ ፫
መለከትን ፡ ንፉ ።
ለእስራኤል ፡ ሥርዓቱ ፡ ነውና ፡ ፬
የያዕቆብም ፡ አምላክ ፡ ሕግ ፡ ነውና ።
ከግብጽ ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ ለዮሴፍ ፡ ምስክር ፡ አቆመው ፡ ፭
ያላወቅሁትን ፡ ቋንቋ ፡ ሰማሁ ።
ጫንቃውን ፡ ከሸክም ፡ ፮
እጆቹንም ፡ በእግር ፡ ብረት ፡ ከመታሠር ፡ አዳንሁ ።
በመከራህ ፡ ጊዜ ፡ ጠራኸኝ ፡ አዳንሁህም ፡ ፯
በተሰወረ ፡ ዐውሎም ፡ መለስሁልህ ፡
በክርክር ፡ ውኃ ፡ ዘንድም ፡ ፈተንሁህ ።
ሕዝቤ ፡ ሆይ ፡ ስማኝ ፡ እነግርሃለሁም ፡ ፰
እስራኤል ፡ ሆይ ፡ እመሰክርልሃለሁ ።
አንተስ ፡ ብትሰማኝ ፡ ሌላ ፡ አምላክ ፡ አይሆንልህም ፡ ፱
ለሌላ ፡ አምላክም ፡ አትስግድም ።
ከግብጽ ፡ ምድር ፡ ያወጣሁህ ፡ ፲
እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክህ ፡ ነኝና ፡
አፍህን ፡ በሰፊው ፡ ክፈት ፡እሞላዋለሁም ።
ሕዝቤ ፡ ግን ፡ ቃሌን ፡ አልሰሙኝም ፡ ፲፩
እስራኤልም ፡ አላዳመጡኝም ።
እንደ ፡ ልባቸው ፡ ሥራ ፡ ተውኋቸው ፡ ፲፪
በልባቸውም ፡ አሳብ ፡ ሄዱ ።

፲፫ ሶበሰ ፡ ሰምዐኒ ፡ ሕዝብየ ፡ ቃልየ ።
ወእስራኤልኒ ፡ ሶበ ፡ ሖሩ ፡ በፍኖትየ ።
፲፬ እምአኅሰርክዎሙ ፡ ለኵሎሙ ፡ ጸላእቶሙ ።
ወእምወደይኩ ፡ እዴየ ፡ ዲበ ፡ እለ ፡ ይሣቅዩዎሙ ።
፲፭ ጸላእቱሰ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሐሰውዎ ።
ወይከውን ፡ ጊዜሆሙ ፡ እስከ ፡ ለዓለም ።
፲፮ ወሴሰዮሙ ፡ ሥብሐ ፡ ሥርናይ ።
ወአጽገቦሙ ፡ መዓረ ፡ እምኰኵሕ ።

---

መዝሙር ፡ ፹፩ ።

ዘለፋ ክህናት ወነገሥት ።

፩ እግዚአብሔር ፡ ቆመ ፡ ውስተ ፡ ማኅበረ ፡ አማልክት።
ወይኬንን ፡ በማእከለ ፡ አማልክት ።
፪ እስከ ፡ ማእዜኑ ፡ ትኬንኑ ፡ ዐመፃ ።
ወታደልዉ ፡ ለገጸ ፡ ኃጥአን ።
፫ ፍትሑ ፡ ለነዳይ ፡ ወለዕጓለ ፡ ማውታ ።
ወአጽድቁ ፡ ግፉዐ ፡ ወምስኪነ ።
፬ ወአድኅኑ ፡ ባሕታዌ ፡ ወጽኑሰ ።
ወአንፍግፍዎሙ ፡ እምእደ ፡ ኃጥአን ።
፭ ኢየአምሩ ፡ ወኢለበዉ ፡ ውስተ፡ጽልመት፡የሐውሩ ።
ወያድለቀልቅ ፡ ኵሉ ፡ መሠረታተ ፡ አድባር ።
፮ አንሰ ፡ እቤ ፡ አማልክት ፡ አንትሙ ።
ወደቂቀ ፡ ልዑል ፡ ኵልክሙ ።
፯ አንትሙሰ ፡ ከመ ፡ ሰብእ ፡ ትመውቱ ።
ወከመ ፡ አሐዱ ፡ እመላእክት ፡ ትወድቁ ።
ተንሥእ ፡ እግዚኦ ፡ ወኰንና ፡ ለምድር ።
እስመ ፡ አንተ ፡ ትወርስ ፡ በኵሉ ፡ አሕዛብ ።

መዝሙር ፡ ፹፪ ።

በእንተ መቃብያን ።

፩ እግዚኦ ፡ መኑ ፡ ከማከ ።
ኢታርምም ፡ ወኢትጸመም ፡ እግዚኦ ።
፪ እስመ ፡ ናሁ ፡ ወውዑ ፡ ፀርከ ።
ወአንሥኡ ፡ ርእሶሙ ፡ ጸላእትከ ።
፫ ወተጓሕለውዎሙ ፡ ምክረ ፡ ለሕዝብከ ።
ወተማከሩ ፡ ዲበ ፡ ቅዱሳኒከ ።
፬ ወይቤሉ ፡ ንዑ ፡ ንሥርዎሙ ፡ እምአሕዛብ ።
ወኢይዝክሩ ፡ እንከ ፡ ስመ ፡ እስራኤል ።
፭ እስመ ፡ ተማከሩ ፡ ኅቡረ ፡ ወዐረዩ ።
ላዕሌከ ፡ ተሰካተዩ ፡ ወተካየዱ ።
ተዓይኒሆሙ ፡ ለኤዶምያስ ፡ ወለእስማኤላውያን ።
፮ ሞአብ ፡ ወአጋራውያን ።
ጌባል ፡ ወዐሞን ፡ ወዐማሌቅ ።
፯ ወኢሎፍሊ ፡ ምስለ ፡ ሰብአ ፡ ጢሮስ ።
፰ አሶርሂ ፡ ኅብረ ፡ ምስሌሆሙ ።
ወኮንዎሙ ፡ ረድኤተ ፡ ለደቂቀ ፡ ሎጥ ።
፱ ረስዮሙ ፡ ከመ ፡ ምድያም ፡ ወሲሳራ ።
ወከመ ፡ ኢያቢስ ፡ በፈለገ ፡ ቂሶን ።
፲ ወይሠረዉ ፡ ከመ ፡ እለ ፡ እንዶር ።
ወይኩኑ ፡ ከመ ፡ መሬተ ፡ ምድር ።
፲፩ ረስዮሙ ፡ ለመላእክቲሆሙ ፡ ከመ ፡ ሄሬብ፡ ወዜብ ።
ወዛብሄል ፡ ወስልማና ፡ ወኵሎሙ ፡ መላእክቲሆሙ።
፲፪ እለ ፡ ይብሉ ፡ ንወርስ ፡ ምሥዋዒሁ ፡ ለእግዚአብሔር
፲፫ አምላኪየ ፡ ረስዮሙ ፡ ከመ ፡ መንኰራኵር ።
ወከመ ፡ ሣዕር ፡ ዘቅድመ ፡ ገጸ ፡ እሳት ።



ሕዝቤስ ፡ ሰምቶኝ ፡ ቢሆን ፡ ፲፫
እስራኤልም ፡ በመንገዴ ፡ ሄዶው ፡ ቢሆን ።
ጠላቶቻቸውን ፡ ፈጥኜ ፡ ባዋረድኋቸው ፡ ነበር ፡ ፲፬
በሚያስጨንቋቸውም ፡ ላይ ፡ እጄን ፡ በዘረጋሁ ፡ ነበር ።
የእግዚአብሔር ፡ ጠላቶችም ፡ በተገዙለት ፡ ነበር ፡ ፲፭
ዘመናቸውም ፡ ለዘላለም ፡ በሆነ ፡ነበር ።
የስንዴውን ፡ ምርት ፡ በሰጣቸው ፡ ነበር ፡ ፲፮
ከዓለቱም ፡ ማር ፡ ባጠገባቸው ፡ ነበር ።

---

መዝሙር ፡ ፹፩ ።

ስለ ፡ ክህናትና ፡ ነገሥታት ፡ በለፋ ።

እግዚአብሔር ፡ በአማልክት ፡ ማኅበር ፡ ቆመ ፡ ፩
በአማልክትም ፡ መካከል ፡ ይፈርዳል ።
እስከ ፡ መቼ ፡ ሐሰትን ፡ ትፈርዳላችሁ ? ፪
እስከ ፡ መቼስ ፡ ለኃጢአተኞች ፡ ፊት ፡ ታደላላችሁ ?
ለድሆችና ፡ ለድሀ ፡ አደጎች፡ ፍረዱ ፡ ፫
ለችግረኛውና ፡ ለምስኪኑ ፡ጽድቅን ፡ አድርጉ ።
ብቸኛውንና ፡ ችግረኛውን ፡ አድኑ ፡ ፬
ከኃጢአተኞችም ፡ እጅ ፡ አስጥሉአቸው ።
አያውቁም ፡ አያስተውሉም ፡ ፭
በጨለማ ፡ ውስጥ ፡ ይመላለሳሉ ።
የምድር ፡ መሠረቶች ፡ ሁሉ ፡ ተናወጡ ።
እኔ ፡ ግን ፡ አማልክት ፡ ናችሁ ፡ ፮
ሁላችሁም ፡ የልዑል ፡ ልጆች ፡ ናችሁ ።
ነገር ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ትሞታላችሁ ፡ ፯
ከአለቆችም ፡ እንደ ፡ አንዱ ፡ ትወድቃላችሁ ፡ አልሁ ።
አቤቱ ፡ ተነሥ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ፍረድ ።
አንተ ፡ አሕዛብን ፡ ሁሉ ፡ ትወርሳለህና ።

መዝሙር ፡ ፹፪ ።

ስለ ፡ መቃብያንና ፡ ስለ ፡ ጎግ ፡ ወማጎግ ።

አቤቱ ፡ እንደ ፡ አንተ ፡ ማን ፡ ነው ? ፩
አቤቱ ፡ ዝም ፡ አትበል ፡ ቸልም ፡ አትበል ።
እነሆ ፡ ጠላቶችህ ፡ ያወካሉና ፡ ፪
የሚጠሉህም ፡ ራሳቸውን ፡ አንሥተዋልና ።
ሕዝብህን ፡ በምክር ፡ ሸንገሉአቸው ፡ ፫
በቅዱሳንህም ፡ ላይ ፡ ተማከሩ ፡
ኑ ፡ ከሕዝብ ፡ መካከል ፡እናጥፋቸው ፡ ፬
ደግሞም ፡ የእስራኤል ፡ ስም ፡ አይታሰብ ፡ አሉ ።
አንድ ፡ ሆነው ፡ በአንተ ፡ ላይ ፡ ተማከሩ ፡ ፭
የኤዶማውያን ፡ ድንኳኖች ፡ እስማኤላውያንም ።
ሞዓብም ፡ አጋራውያንም ፡ ፮
ጌባል ፡ አሞንም ፡ አማሌቅም ።
ፍልስጥኤማውያንም ፡ ከጢሮስ፡ ሰዎች ፡ ጋር ፡ ፯
በአንተ ፡ ላይ ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አደረጉ ።
አሦርም ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ተባበረ ፡ ፰
ለሎጥ ፡ ልጆችም ፡ ረዳት ፡ ሆኗቸው ።
እንደ ፡ ምድያምና ፡ እንደ ፡ ሲሣራ ፡ ፱
በቂሶንም ፡ ወንዝ ፡ እንደ ፡ ኢያቢስ ፡ አድርግባቸው ።
በዓይንዶር ፡ ጠፉ ፡ ፲
እንደ ፡ ምድርም ፡ ጕድፍ ፡ ሆኑ ።
አለቆቻቸውን ፡ እንደ ፡ ሔሬብና ፡ እንደ ፡ ዜብ ፡ ፲፩
ታላላቆቻቸውንም ፡ እንደ፡ዛብሄልና፡ እንደ፡ስልማና፡
አድርጋቸው ።
የእግዚአብሔርን ፡ መሠዊያ፡ እንወርሳለን፡የሚሉትን ፡ ፲፪
አምላኬ ፡ ሆይ ፡ እንደ ፡ ትቢያ ፡ ፲፫
በነፋስ ፡ ፊትም ፡ እንደ ፡ ገለባ ፡ አድርጋቸው ።

፲፬ ወከመ ፡ እሳት ፡ ዘያውዒ ፡ ገዳመ ።
ወከመ ፡ ነበልባል ፡ ዘያነድድ ፡ አድባረ ።
፲፭ ከማሁ ፡ ስድዶሙ ፡ በዐውሎከ ።
ወሁከሙ ፡ በመቅሠፍትከ ።
፲፮ ምላዕ ፡ ውስተ ፡ ገጾሙ ፡ ኀሳረ ።
ወያእምሩ ፡ ስመከ ፡ እግዚኦ ።
፲፯ ይትኀፈሩ ፡ ወይትሀወኩ ፡ ለዓለም ።
ይኅሰሩ ፡ ወይትኀጐሉ ።
፲፰ ወያእምሩ ፡ ስመከ ፡ እግዚኦ ።
ከመ ፡ አንተ ፡ ባሕቲትከ ፡ ልዑል ፡ ዲበ ፡ ኵሉ ፡
ምድር ።

መዝሙር ፡ ፹፫ ።

በእንተ ትሩፋን ።

፩ ጥቀ ፡ ፍቁር ፡ አብያቲከ፡እግዚኦ፡ እግዚአ፡ኃያላን ።
፪ ተፈሥሐት ፡ ነፍስየ፡በአፍቅሮ፡አዕጻዲከ ፡ እግዚኦ ።
ልብየኒ ፡ ወሥጋየኒ፡ተፈሥሓ፡ በእግዚአብሔር ሕያው
፫ ዖፍኒ ፡ ረከበት ፡ ላቲ ፡ ቤተ ።
ወማዕነቅኒ ፡ ኀበ ፡ ታነብር ፡ ዕጐሊሃ ።
ምሥዋዒከ ፡ እግዚኦ ፡ እግዚአ ፡ ኀያላን ።
ንጉሥየኒ ፡ ወአምላኪየኒ ።
፬ ብፁዓን ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይነብሩ ፡ ውስተ ፡ ቤትከ ።
ወለዓለመ ፡ ዓለም ፡ ይሴብሑከ ።
፭ ብፁዕ ፡ ብእሲ ፡ ዘእምኀቤከ ፡ ረድኤቱ ፡ እግዚኦ ።
ወዘይሔሊ ፡ በልቡ ፡ ዘበላዕሉ ።
፮ ውስተ ፡ ቈላተ ፡ ብካይ ፡ ብሔር ፡ ኀበ ፡ ሠራዕኮሙ ።
እስመ ፡ መምህረ ፡ ሕግ ፡ ይሁብ ፡ በረከተ ።
፯ ወየሐውር ፡ እምኀይል ፡ ውስተ ፡ ኀይል ።
ወያስተርኢ ፡ አምላከ ፡ አማልክት ፡ በጽዮን ።
፰ እግዚኦ ፡ አምላከ ፡ ኀያላን ፡ ስምዐኒ ፡ ጸሎትየ ።
ወአጽምዐኒ ፡ አምላኩ ፡ ለያዕቆብ ።
፱ ወርኢየኒ ፡ እግዚኦ ፡ ተአምኖትየ ።
ወነጽር ፡ ኀበ ፡ ገጸ ፡ መሢሕከ ።
፲ እስመ ትኄይስ አሐቲ ዕለት ውስተ አዕጻዲከ እምአእላፍ ።
አብደርኩ ፡ እትገደፍ ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ እግዚአብሔር ።
እምእንበር ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ ኃጥአን ።
፲፩ እስመ ፡ ጽድቀ፡ወምጽዋተ ፡ ያበድር፡ እግዚአብሔር ።
እግእዚብሔር ፡ ይሁብ ፡ ክብረ ፡ ወሞገሰ ።
እግዚአብሔር ፡ ኢያስተጸንሶሙ ፡ እምበረከቱ፡ለእለ
የሐውሩ ፡ በየዋሃት ።
፲፪ እግዚኦ ፡ አምላከ ፡ ኀያላን ።
ብፁዕ ፡ ብእሲ ፡ ዘተወከለ ፡ ኪያከ ።

መዝሙር ፡ ፹፬ ።

በእንተ ትሩፋን ።

፩ ተሣሀልከ፡ እግዚኦ ፡ ምድረከ ።
ወሜጥከ ፡ ፄዋሁ ፡ ለያዕቆብ ።
፪ ወኀደገ ፡ ኀጢአቶሙ ፡ ለሕዝብከ ።
ወከደንከ ፡ ኵሎ ፡ አበሳሆሙ ።
፫ ወኀደገ ፡ ኵሎ ፡ መዓተከ ።
ወሜጥከ ፡ መቅሠፍተ ፡ መዓትከ ።
፬ ሚጠነ ፡ እምላክነ ፡ ወመድኀኒነ ።
ወሚጥ ፡ መዓተከ ፡ እምኔነ ።
፭ ወለዓለምሁ ፡ ኢትትመዐዐነ ።
ወኢታንኅ ፡ መዓተከ ፡ ላዕለ ፡ትውልደ ፡ ትውልድ ።



እሳት ፡ ዱርን ፡ እንደሚያቃጥል ፡ ፲፬
ነበልባልም ፡ ተራሮችን ፡ እንደሚያነድ ።
እንዲሁ ፡ በቍጣህ ፡ አንዳቸው ፡ ፲፭
በመቅሠፍትህም ፡ አስደንግጣቸው ።
ፊታቸውን ፡ ኃፍረት ፡ ሙላው ፡ ፲፮
አቤቱ ፡ ስምህንም ፡ ይፈልጋሉ ።
ይፈሩ ፡ ለዘላለሙም ፡ ይታወኩ ፡ ፲፯
ይጐስቍሉ ፡ ይጥፉም ።
ስምህም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ፲፰
በዓለም ፡ ሁሉ ፡ ላይም ፡ አንተ ፡ ብቻ ፡ ልዑል ፡ እንደ ፡
ሆንህ ፡ ይወቁ ።

መዝሙር ፡ ፹፫ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ ማደሪያዎችህ ፡ እንደምን ፡ ፩
የተወደዱ ፡ ናቸው ፡
ነፍሴ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ አደባባዮች ፡ ትወዳለች ፡
ትናፍቅማለች ፡ ፪
ልቤም ፡ ሥጋዬም ፡ በሕያው ፡ አምላክ ፡ ደስ ፡ ተሰኘ ።
ወፍ ፡ ለእርሷ ፡ ቤትን ፡ አገኘች ፡ ፫
ዋኖስም፡ ጫጩቶችዋን ፡ የምታኖርበት ፡ ቤት፡ አገኘች ።
የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ ንጉሤም ፡ አምላኬም ፡ ሆይ ፡
እርሱ ፡ መሠዊያህ ፡ ነው ።
በቤትህ ፡ የሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡ የተመሰገኑ ፡ ናቸው ፡ ፬
ለዓለምና ፡ ለዘላለምም ፡ ያመሰግኑሃል ።
አቤቱ ፡ እርዳታው ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡ የሆነለት ፡ ፭
በልቡም ፡ የላይኛውን ፡ መንገድ ፡ የሚያስብ ፡ ሰው ፡
ምስጉን ፡ ነው ።
በልቅሶ ፡ሸለቆ ፡ ውስጥ ፡ በወሰነው ፡ ሥፍራ ፡ ፮
የሕግ ፡ መምህር ፡ በረከትን ፡ ይሰጣልና ።
ከኃይል ፡ ወደ ፡ ኃይል ፡ ይሄዳል ፡ ፯
የአማልክት ፡ አምላክ ፡ በጽዮን ፡ ይታያል ።
የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ አቤቱ ፡ ጸሎቴን ፡ ስማ ፡ ፰
የያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ አድምጥ ።
አቤቱ ፡ መታመኛችንን ፡ እይልን ፡ ፱
ወደ ፡ መሢሕህም ፡ ፊት ፡ ተመልከት ።
ከአእላፍ፡ይልቅ፡በአደባባዮችህ፡አንዲት፡ቀን፡ትሻላለች፡ ፲
በኃጥአን ፡ ድንኳኖች ፡ ከመቀመጥ ፡ ይልቅ ፡
በእግዚአብሔር፡ ቤት ፡ ደጅ ፡ እጣል ፡ ዘንድ ፡ መረጥሁ ።
እግዚአብሔር ፡አምላክ፡ምሕረትንና፡እውነትን፡ ስለወደደ፡ ፲፩
ሞገስንና ፡ ክብርን ፡ ይሰጣል ።
እግዚአብሔር ፡ በቅንነት ፡ የሚሄዱትን ፡
ከመልካም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አያሳጣቸውም ።
የሠራዊት ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ ፲፪
በአንተ ፡ የታመነ ፡ ሰው ፡ ምስጉን ፡ ነው ።

መዝሙር ፡ ፹፬ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ፡ መመለስ ።

አቤቱ ፡ ለምድርህ ፡ ሞገስን ፡ አደረግህ ፡ ፩
የያዕቆብንም ፡ ምርኮ ፡ መለስህ ።
የሕዝብህን ፡ ኃጢአት ፡ አስቀረህ ፡ ፪
አበሳቸውንም ፡ ሁሉ ፡ ከደንህ ።
መዓትህንም ፡ ሁሉ ፡ አስወገድህ ፡ ፫
ከቍጣህ ፡ መቅሠፍት ፡ ተመለስህ ።
የመድኃኒታችን ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ መልሰን ፡ ፬
ቍጣህንም ፡ ከእኛ ፡ መልስ ።
በውኑ ፡ ለዘላለም ፡ ትቆጣናለህን ? ፭
ቍጣህንስ ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ታስረዝማለህን ?

፮ አንተ ፡ አምላክነ ፡ ተመየጠነ ፡ ወአሕይወነ ።
ወሕዝብከኒ ፡ ይትፌሥሑ ፡ ብከ ።
፯ አርእየነ ፡ እግዚኦ ፡ ሣህለከ ።
ወሀበነ ፡ አምላክነ ፡ አድኅኖተከ ።
፰ እጸምዕ ፡ ዘይነብበኒ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላኪየ ።
እስመ ፡ ይነብብ ፡ ሰላመ ፡ ላዕለ ፡ ሕዝቡ ።
ላዕለ ፡ ጻድቃኑ፡ወላዕለ፡እለ፡ይመይጡ፡ልቦሙ፡ኀቤሁ።
ወባሕቱ ፡ ቅሩብ ፡ አድኅኖቱ ፡ ለእለ ፡ ይፈርህዎ ።
፱ ከመ ፡ ይኅድር ፡ ስብሐቲሁ ፡ ውስተ ፡ ምድርነ ።
፲ ሣህል ፡ ወርትዕ ፡ ተራከባ ።
ጽድቅ ፡ ወሰላም ፡ ተሰዐማ ።
፲፩ ርትዕሰ፡ እምድር ፡ ሠረጸት ።
ወጽድቅኒ ፡ እምሰማይ ፡ ሐወጸ ።
፲፪ እግዚአብሔርኒ ፡ ይሁብ ፡ ምሕረቶ ።
ምድርኒ ፡ ትሁብ ፡ ፍሬሃ ።
፲፫ ጽድቅ ፡ የሐውር ፡ ቅድሜሁ ።
ወየኀድግ ፡ ውስተ ፡ ፍኖት ፡ አሠሮ ።

መዝሙር ፡ ፹፭ ።
በእንተ ሕዝቅያስ ።

፩ እጽምዕ ፡ እግዚኦ ፡ እዝነከ ፡ ኀቤየ ፡ ወስምዐኒ ።
እስመ ፡ ነዳይ ፡ ወምስኪን ፡ አነ ።
፪ ዕቀባ ፡ ለነፍስየ ፡ እስመ ፡ የዋህ ፡ አነ ።
አድኅኖ ፡ ለገብርከ ፡ አምላኪየ ፡ ዘተወከለ ፡ ኪያከ ።
፫ ተሣሀለኒ ፡ እግዚኦ ፡ እስመ ፡ ኀቤከ፡እጸርኅ፡ኵሎ፡እሚረ
፬ ወአስተፍሥሒ ፡ ለነፍሰ ፡ ገብርከ ።
እስመ ፡ ኀቤከ ፡ አንቃዕዶኩ ፡ ነፍስየ ።
፭ እስመ ፡ መሓሪ ፡ አንተ ፡ እግዚኦ ፡ ወመስተሣህል ።
ወብዙኅ ፡ ሣህልከ ፡ ለኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይጼውዑከ ።
፮ አጽምዕ ፡ እግዚኦ ፡ ጸሎትየ ።
ወነጽር ፡ ቃለ ፡ ስእለትየ ።
፯ በዕለተ ፡ ምንዳቤየ፡ጸራኅኩ፡ኀቤከ፡እስመ፡ሰማዕከኒ ።
፰ አልቦ ፡ ዘይመስለከ ፡ እምነ ፡ አማልክት ፡ እግዚኦ ።
ወአልቦ ፡ ዘከመ ፡ ምግባሪከ ።
፱ ኵሎሙ ፡ አሕዛብ ፡ እለ ፡ ገበርከ ፡ ይምጽኡ ።
ወይስግዱ ፡ ቅድሜከ ፡ እግዚኦ ።
ወይሰብሑ ፡ ለስምከ ።
፲ እስመ ፡ ዐቢይ ፡ አንተ፡እግዚኦ፡ዘትገብር፡መንክረ ።
አንተ ፡ እግዚአብሔር ፡ባሕቲትከ ፡ ዐቢይ ።
፲፩ ምርሐኒ ፡ እግዚኦ ፡ ፍኖተከ ። ወአሖር ፡ በጽድቅከ ።
ይትፌሣሕ ፡ ልብየ ፡ ለፈሪሀ ፡ ስምከ ።
፲፪ እገኒ ፡ ለከ ፡ እግዚኦ ፡ በኵሉ ፡ ልብየ ፡ አምላኪየ ።
ወእሴብሕ ፡ ለስምከ ፡ ለዓለም ።
፲፫ እስመ ፡ ዐብየት ፡ ምሕረትከ ፡ ላዕሌየ ።
ወአድኀንከ ፡ ለነፍስየ ፡ እምሲኦል ፡ ታሕቲት ።
፲፬ አምላኪየ ፡ ዐማፅያን ፡ ቆሙ ፡ ላዕሌየ ።
ወማኅበረ ፡ እኩያን ፡ ኀሠሥዋ ፡ ለነፍስየ ።
ወኢረሰዩከ ፡ ቅድሜሆሙ ።
፲፭ አንተሰ ፡ እግዚኦ ፡ መሓሪ ፡ ወመስተሣህል ።
ርኁቀ ፡ መዓት ፡ ወብዙኅ ፡ ምሕረት ፡ ወጻድቅ ።
፲፮ ነጽር ፡ ላዕሌየ ፡ ወተሣሀለኒ ።
ሀብ ፡ ኀይለ ፡ ለገብርከ ።
ወአድኅኖ ፡ ለወልደ ፡ አመትከ ።
፲፯ ግበር ፡ ምስሌነ ፡ ትእምርተ ፡ ለሠናይ ።
ይርአዩ ፡ ጸላእትነ ፡ ወይትኀፈሩ ።
ከመ ፡ አንተ ፡ እግዚኦ ፡ ረዳእከነ ፡ ወአስተፍሣሕከነ ።



አቤቱ ፡ ትመለሳለህ ፡ ታድነንማለህ ፡ ፮
ሕዝብህም ፡ በአንተ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
አቤቱ ፡ ምሕረትህን ፡ አሳየን ፡ ፯
አቤቱ ፡ መድኃኒትህንም ፡ ስጠን ።
እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ የሚናገረውን ፡ እሰማለሁ ፡ ፰
ሰላምን ፡ ለሕዝቡና ፡ ለቅዱሳኑ ፡
ልባቸውንም ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ለሚመልሱ ፡ ይናገራልና ።
ነገር ፡ ግን ፡ ክብር ፡ በምድራችን ፡ ያድር ፡ ዘንድ ፡ ፱
ማዳኑ ፡ ለሚፈሩት ፡ ቅርብ ፡ ነው ።
ምሕረትና ፡ እውነት ፡ ተገናኙ ፡ ፲
ጽድቅና ፡ ሰላም ፡ ተስማሙ ።
እውነት ፡ ከምድር ፡ በቀለች ፡ ፲፩
ጽድቅም ፡ ከሰማይ ፡ መጣች ።
እግዚአብሔርም ፡ በጎ ፡ ነገርን ፡ ይሰጣል ፡ ፲፪
ምድራችንም ፡ ፍሬዋን ፡ ትሰጣለች ።
ጽድቅ ፡ በፊቱ ፡ ይሄዳል ፡ ፲፫
ፍለጋውንም ፡ በመንገድ ፡ ውስጥ ፡ ያኖራል ።

መዝሙር ፡ ፹፭ ።
ስለ ፡ ሕዝቅያስ ።

አቤቱ፡ ጆሮህን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አዘንብል ፡ አድምጠኝም ፡ ፩
ችግረኛና ፡ ምስኪን ፡ ነኝና ።
ቅዱስ ፡ ነኝና ፡ ነፍሴን ፡ ጠብቅ ፡ ፪
አምላኬ፡ ሆይ፡ አንተን፡ የታመነውን፡ ባሪያህን፡ አድነው።
አቤቱ፡ ቀኑን፡ ሁሉ ፡ ወደ፡ አንተ፡ እጮኻለሁና ፡ ማረኝ። ፫
የባሪያህን ፡ ነፍስ ፡ ደስ፡ አሰኛት ፡ ፬
አቤቱ ፡ ነፍሴን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ አንሥቻለሁና ።
አቤቱ ፡ አንተ ፡ መሓሪና ፡ ይቅር፡ባይ ፡ ነህና ፡ ፭
ምሕረትህም ፡ ለሚጠሩህ ፡ ሁሉ ፡ ብዙ ፡ ነውና ።
አቤቱ ፡ ጸሎቴን ፡ አድምጥ ፡ ፮
የልመናዬንም ፡ ድምፅ ፡ ስማ ።
ትመልስልኛለህና፡በመከራዬ፡ቀን፡ ወደንተ፡ እጠራለሁ ። ፯
አቤቱ ፡ ከአማልክት ፡ የሚመስልህ ፡ የለም ፡ ፰
እንደ ፡ ሥራህም ፡ ያለ ፡ የለም ።
የፈጠርሃቸው ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ይመጣሉ ፡ ፱
አቤቱ ፡ በፊትህም ፡ ይሰግዳሉ ፡
ስምህንም ፡ ያከብራሉ ።
አቤቱ ፡ ድንቅ ፡ የምታደርግ ፡ አንተ ፡ ታላቅ ፡ ነህና ፡ ፲
አንተም ፡ ብቻህን ፡ ታላቅ ፡ አምላክ ፡ ነህና ።
አቤቱ ፡ መንገድህን ፡ ምራኝ ፡ ፲፩
በእውነትህም ፡ እሄዳለሁ ፡
ስምህን ፡ ለመፍራት ፡ ልቤ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ።
አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ ሆይ፡በልቤ ፡ ሁሉ ፡ አመሰግንሃለሁ ፡ ፲፪
ለዘላለምም ፡ ስምህን ፡ አከብራለሁ ።
ምሕረትህ ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ታላቅ ፡ ናትና ፡ ፲፫
ነፍሴንም ፡ ከታችኛይቱ ፡ ሲኦል ፡ አድነሃታልና ።
አቤቱ ፡ ዓመፀኞች ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ተነሥተዋል ፡ ፲፬
የክፉዎችም ፡ ማኅበር ፡ ነፍሴን ፡ ይፈልጓታል ፡
በፊታቸውም ፡ አላደረጉህም ።
አቤቱ ፡ አንተ ፡ ግን ፡ መሓሪና፡ ርኅሩኅ ፡ አምላክ ፡ ነህ ፡ ፲፭
መዓትህ፡ የራቀ ፡ ምሕረትህና፡ ቸርነትህም፡ የበዛ፡ ነህና ።
ወደ ፡ እኔ ፡ ተመልከት ፡ ማረኝም ፡ ፲፮
ለባሪያህ ፡ ኃይልን ፡ ስጥ ፡ የሴት ፡ ባሪያህንም ፡ ልጅ ፡ አድን ።
ምልክትንም ፡ ለመልካም ፡ ነገር፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡አድርግ ፡ ፲፯
የሚጠሉኝ ፡ ይዩ ፡ ይፈሩም ፡
አቤቱ ፡ አንተ ፡ ረድተኸኛልና ፡ አጽንተኸኛልምና ።

መዝሙር ፡ ፹፯ ።

በእንተ ሕዝቅያስ ወበእንተ

፩ መሠረታቲሃ ፡ ውስተ ፡ አድባር ፡ ቅዱሳን ።
ያበድሮን ፡ እግዚአብሔር ፡ ለአናቅጸ ፡ ጽዮን ።
፪ እምኵሉ ፡ ተዓይኒሁ ፡ ለያዕቆብ ።
፫ ነኪር ፡ ነገሩ ፡ በእንቲአኪ ፡ ሀገረ ፡ እግዚአብሔር ።
፬ እዜክሮን ፡ ለረዐብ ፡ ወለባቢሎን ፡ እለ ፡ የአምራኒ ።
ወናሁ ፡ ኢሎፍሊ ፡ ወጢሮስ ፡ ወሕዝበ ፡ ኢትዮጵያ ።
እለ ፡ ተወልዱ ፡ በህየ ።
፭ እምነ ፡ ጽዮን ፡ ይብል ፡ ሰብእ ።
ወብእሲ ፡ ተወልደ ፡ በውስቴታ ።
ወውእቱ ፡ ልዑል ፡ ሣረራ ።
፮ እግዚአብሔር ፡ ይነግሮሙ ፡ ለሕዝቡ ፡ በመጽሐፍ ።
ወለመላእክቲሆሙ ፡ እለ ፡ ተወልዱ ፡ በውስቴታ ።
፯ ከመ ፡ ፍሡሐን ፡ ኵሎሙ ፡ እለ፡ይነብሩ፡ውስቴትኪ ።

መዝሙር ፡ ፹፰ ።

በእንተ ትሩፋን ።

፩ እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ መድኃኒትየ ።
ዕለትየ ፡ ጸራኅኩ ፡ ኀቤከ ፡ ወሌሊትየኒ ፡ ቅድሜከ ።
፪ ለትባእ ፡ ጸሎትየ ፡ ቅድሜከ ።
አጽምዕ ፡ እዝነከ ፡ ኀበ ፡ ስእለትየ ።
፫ እስመ ፡ ጸግበት ፡ ነፍስየ ፡ ሕማመ ።
ወአልጸቀት ፡ ለሞት ፡ ሕይወትየ ።
፬ ወተኈለቁ ፡ ምስለ ፡ እለ ፡ ይወርዱ ፡ ውስተ፡ ዐዘቅት ።
ወኮንኩ ፡ ከመ ፡ ብእሲ ፡ ዘአልቦ ፡ ረዳኢ ።
ግዑዘ ፡ ውስተ ፡ ምዉታን ።
ከመ ቅቱላን ወግዱፋን እለ ይሰክቡ ውስተ መቃብር ።
፭ እለ ፡ ኢዘከርኮሙ ፡ ለግሙራ ።
እስመ ፡ እሙንቱሂ ፡ ርኁቁ ፡ እምእዴከ ።
ወአንበሩኒ ፡ ውስተ ፡ ዐዘቅት ፡ ታሕት ።
፮ ውስተ ፡ ጽልመት ፡ ወጽላሎተ ፡ ሞት ።
፯ ላዕሌየ ፡ ጸንዐ ፡ መዓትከ ።
ወኵሎ ፡ መቅሠፍተከ ፡ አምጻእከ ፡ ላዕሌየ ።
፰ አርኀቀ ፡ እምኔየ ፡ እለ ፡ የአምሩኒ ።
ወረሰይከኒ ፡ ርኩሰ ፡ በኀቤሆሙ ።
ወአኀዙኒ ፡ አልብየ ፡ ሙፃአ ።
፱ ወአዕይንትየኒ ፡ ደክማ ፡ በተጽናስ ።
ወጸራኅኩ ፡ ኀቤከ ፡ እግዚኦ ።
ወኵሎ ፡ አሚረ ፡ አንሥአ ፡ እደውየ ፡ ኀቤከ ።
፲ ቦኑ ፡ ለምዉታን ፡ ትገብር ፡ መንክረከ ።
ወዐቀብተ ፡ ሥራይኑ ፡ ያነሥኡ ።
፲፩ ወይነግሩኑ ፡ እለ ፡ ውስተ ፡ መቃብር ፡ ሣህለከ ።
ወጽድቀከኒ ፡ ውስተ ፡ ሞትኑ ።
፲፪ ይትዐወቅኑ ፡ ውስተ ፡ ጽልመት ፡ መንክርከ ።
ወርትዕከኒ ፡ በምድርኑ ፡ ተረስዐ ።
፲፫ ወአነሂ ፡ እግዚኦ ፡ ኀቤከ ፡ ጸራሕኩ ።
በጽባሕ ፡ ትብጻሕከ ፡ ጸሎትየ ።
፲፬ ለምንት ፡ እግዚኦ ፡ ትገድፍ ፡ ጸሎትየ ።
ወትመይጥ ፡ ገጸከ ፡ እምኔየ ።
፲፭ ነዳይ ፡ አነ ፡ ሠራሕኩ ፡ እምንእስየ ።
ተልዒልየ ፡ ተትሕትኩ ፡ ወተመነንኩ ።
፲፮ ላዕሌየ ፡ ኀለፈ ፡ መቅሠፍትከ ።
ወግርማከ ፡ አደንገጸኒ ።
፲፯ ዐገቱኒ ፡ ኵሎ ፡ አሚረ ፡ ከመ፡ ማይ። ወአኀዙኒ፡ኅቡረ።



መዝሙር ፡ ፹፯ ።

ስለ ፡ ሕዝቅያስና ፡ ስለ ፡ አመቤታችን ።

መሠረቶቹ ፡ በተቀደሱ ፡ ተራሮች ፡ ናቸው ፡ ፩
ከያዕቆብ ፡ ድንኳኖች ፡ ይልቅ ፡ ፪
እግዚአብሔር ፡ የጽዮንን ፡ ደጆች ፡ ይወዳቸዋል ።
የእግዚአብሔር ፡ ከተማ ፡ ሆይ ፡ በአንቺ ፡ የተከበረ ፡ ፫
ነገር ፡ ይደረጋል ፡ ይባላል ።
የሚያውቁኝን ፡ረዓብንና ፡ ባቢሎንን ፡ አስባቸዋለሁ ፡ ፬
እነሆ ፡ ፍልስጥኤማውያን ፡ ጢሮስም ፡ ሕዝብ ።
እነዚህ ፡ በዚያ ፡ ተወለዱ ።
ሰው ፡ ጽዮንን ፡ እናታችን ፡ ይላታል ፡ ፭
በውስጧም ፡ ሰው ፡ ተወለደ ፡
እርሱ ፡ ራሱም ፡ ልዑል ፡ መሠረታት ።
እግዚአብሔር ፡ ለሕዝቡ ፡ ፮
በውስጧም ፡ ለተወለዱት ፡ አለቆቿ ።
በመጽሐፍ ፡ ይነግራቸዋል ።
በአንቺ ፡ የሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ እንደሚላቸው ፡ ይነግራቸዋል ። ፯

መዝሙር ፡ ፹፰ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

አቤቱ ፡ የመድኃኒቴ ፡ አምላክ ፡ ፩
በቀንና ፡ በሌሊት ፡ በፊትህ ፡ ጮኽሁ ፡
ጸሎቴ ፡ ወደ ፡ ፊትህ ፡ ትግባ ፡ ፪
ጆሮህንም ፡ ወደ ፡ ጩኸቴ ፡ አዘንብል ፡
ነፍሴ ፡ መከራን ፡ ጠግባለችና ፡ ፫
ሕይወቴም ፡ ወደ ፡ ሲኦል ፡ ቀርባለችና ።
ወደ፡ጕድጓድ ፡ ከሚወርዱ ፡ ጋር ፡ ተቆጠርሁ ፡ ፬
ረዳትም ፡ እንደሌለው ፡ ሰው ፡ ሆንሁ ።
ስዘላለም ፡ እንደማታስባቸው ፡ ፭
እንደ ፡ ተገደሉና ፡ በመቃብር ፡ ውስጥ፡እንደ ፡ ተጣሉ ፡
በሙታን ፡ ውስጥ ፡ እንዳሉ ፡ የተጣልሁ ፡ ሆንሁ ፡
እነርሱም ፡ ከእጅህ ፡ ተለዩ ።
በጨለማና ፡ በሞት ፡ ጥላ ፡ ውስጥ ፡ ፮
በታችኛው ፡ ጕድጓድ ፡ አስቀመጥኸኝ ።
በእኔ ፡ ላይ ፡ ቍጣህ ፡ ጸና ፡ ፯
መቅሠፍትህን ፡ ሁሉ ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ አመጣህ ።
የሚያውቁኝን ፡ ከእኔ ፡ አራቅህ ፡ ፰
በእነርሱ ፡ ዘንድ ፡ ርኵስ ፡ አደረግኸኝ ፡
ያዙኝ ፡ መውጫም ፡ አሳጡኝ ።
ዓይኖቼም ፡ በመከራ ፡ ፈዘዙ ፡ ፱
አቤቱ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ጮኽሁ ።
እጆቼንም ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ዘረጋሁ ።
በውኑ ፡ ለሙታን ፡ ተአምራት ፡ ታደርጋለህን ፡ ፲
የሞቱትስ ፡ ተነሥተው ፡ ያመሰግኑሃልን ?
በመቃብርስ ፡ ውስጥ ፡ ቸርነትህን ፡ ፲፩
እውነትህንስ ፡ በጥፋት ፡ ስፍራ ፡ ይናገሩሉን ።
ተአምራትህ ፡ በጨለማ ፡ ፲፪
ጽድቅህም ፡ በመረሳት ፡ ምድር ፡ ትታወቃለችን ?
አቤቱ ፡ እኔ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ጮኽሁ ፡ ፲፫
ጧት ፡ ጸሎቴ ፡ ወደ ፡ ፊትህ ፡ ትደርሳለች ።
አቤቱ ፡ ነፍሴን ፡ ለምን ፡ ትጥላለህ ? ፲፬
ፊትህንስ ፡ ከእኔ ፡ ለምን ፡ ትሰውራለህ ?
እኔ ፡ ከታናሽነቴ ፡ ችግረኛ፡ ለሞትም፡ የቀረብሁ ፡ ነኝ ፡ ፲፭
ከፍ ፡ ከፍ፡ ካልሁ ፡ በኋላ፡ ግን፡ ተዋረድሁ፡ ተናቅሁም ።
መቅሠፍትህ ፡ በላዩ ፡ አለፈ ፡ ፲፮
ግርማህም ፡ አስደነገጠኝ ።
ሁል ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ውኃ ፡ ከበቡኝ ፡ ፲፯
በአንድነትም ፡ ያዙኝ ።

፲፰ አርኀቀ ፡ እምኔየ ፡ አዕርክትየ ፡ ወቢጽየ ።
ወአዝማድየ ፡ እምተጽናስየ ።

መዝሙር ፡ ፹፰ ።

በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ ምሕረተከ ፡ እሴብሕ ፡ እግዚኦ ፡ ለዓለም ።
ወእዜኑ ፡ ጽድቀከ ፡ በአፉየ ፡ ለትውልደ ፡ ትውልድ ።
፪ እስመ ፡ ትቤ ፡ ለዓለም ፡ እሐንጽ ፡ ምሕረተ ።
በሰማይ ፡ ጸንዐ ፡ ጽድቅከ ።
፫ ኪዳነ ፡ ተካየድኩ ፡ ምስለ ፡ ኅሩያንየ ።
ወመሐልኩ ፡ ለዳዊት ፡ ገብርየ ።
፬ ለዓለም ፡ አስተዴሉ ፡ ዘርዐከ ።
ወእሐንጽ ፡ ለትውልደ ፡ ትውልድ ፡ መንበረከ ።
፭ ይገንያ ፡ ሰማያት ፡ ለስብሐቲከ ፡ እግዚኦ ።
ወጽድቀከኒ ፡ በማኅበረ ፡ ቅዱሳን ።
፮ መኑ ፡ ይትዔረዮ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በደመናት ።
ወመኑ ፡ ይመስሎ ፡ ለእግዚአብሔር ለምደቂቀ ፡ አማልክት ።
፯ እግዚአብሔር ፡ ስቡሕ ፡ በምክረ ፡ ቅዱሳን ።
ዐቢይ ፡ ወግሩም ፡ ዲበ ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ ዐውዱ ።
፰ እግዚኦ ፡ አምላከ ፡ ኀያላን ፡ መኑ ፡ ከማከ ።
ኀያል ፡ አንተ ፡ እግዚኦ ፡ ወጽድቅ ፡ የዐውደከ ።
፱ አንተ ፡ ትኴንን ፡ ኃይለ ፡ ባሕር ።
ወአንተ ፡ ታረምም ፡ ለድምፀ ፡ ማዕበላ ።
፲ አንተ ፡ አኅሰርኮ ፡ ለዕቡይ ፡ ከመ ፡ ቅቱል ።
ወበመዝራዕተ ፡ ኃይልከ ፡ ዘረውኮሙ ፡ ለፀርከ ።
፲፩ ዚአከ ፡ ውእቱ ፡ ሰማያት፡ወአንቲአከ፡ይእቲ፡ምድር ።
ወዓለመኒ ፡ በምልዑ ፡ አንተ ፡ ሣረርከ ።
፲፪ ባሕረ ፡ ወመስዐ ፡ ዘአንተ ፡ ፈጠርከ ።
ታቦር ፡ ወአርሞንኤም ፡ በስመ ፡ ዚአከ ፡ ይትፌሥሑ።
ወይሴብሑ ፡ ለስምከ ።

፲፫ መዝራዕትከ ፡ ምስለ ፡ ኀይል ።
ጽንዐት ፡ እዴከ ፡ ወተለዐለት ፡ የማንከ ።
፲፬ ፍትሕ ፡ ወርትዕ ፡ ተድላ ፡ መንበርከ ።
ሣህል ፡ ወጽድቅ ፡ የሐውር ፡ ቅድመ ፡ ገጽከ ።
፲፭ ብፁዕ ፡ ሕዝብ ፡ ዘየአምር ፡ የብቦ ።
እግዚኦ ፡ በብርሃነ ፡ ገጽከ ፡ የሐውሩ ።
፲፮ ወበስምከ ፡ ይትፌሥሑ ፡ ኵሎ ፡ አሚረ ።
ወበጽድቅከ ፡ ይትሌዐሉ ።
፲፯ እስመ ፡ ምክሐ ፡ ኀይሎሙ ፡ አንተ ።
ወበሣህልከ ፡ ይትሌዐል ፡ ቀርንነ ።
፲፰ እስመ ፡ ዘእግዚአብሔር ፡ ረድኤትነ ።
ወቅዱስ ፡ እስራኤል ፡ ንጉሥነ ።
፲፱ ውእተ ፡ አሚረ ፡ ተናገርኮሙ ፡ በራእይ ፡ ለደቂቅከ ።
ወትቤ ፡ እሬሲ ፡ ረድኤተ ፡ በላዕለ ፡ ኀይል ።
ወአልዐልኩ ፡ ኅሩይየ ፡ እምሕዝብየ ።
፳ ወረከብክዎ ፡ ለዳዊት ፡ ገብርየ ።
ወቀባዕክዎ ፡ ቅብዐ ፡ ቅዱስ ።
፳፩ እስመ ፡ እዴየ ፡ ትረድኦ ፡ ወመዝራዕትየ ፡ ታጸንዖ ።
፳፪ ወኢይበቍዖ ፡ ጸላዒ ፡ በላዕሌሁ ።
ወውሉደ ፡ ዐመፃ ፡ ኢይደግም ፡ አሕምሞቶ ።
፳፫ ወእመትሮሙ ፡ ለፀሩ ፡ እምቅድመ ፡ ገጹ ።
ወእኀስሮሙ ፡ ለጸላእቱ ።
፳፬ ወሣህልየሰ ፡ ወጽድቅየ ፡ ምስሌሁ ።
ወበስምየ ፡ ይትሌዐል ፡ ቀርኑ ።
፳፭ ወእሠይም ፡ ውስተ ፡ ባሕር ፡ እዴሁ ።
ወውስተ ፡ አፍላግ ፡ የማኖ ።
፳፮ ወውእቱ ፡ ይብለኒ ፡ አቡየ ፡ አንተ ።
አምላኪየ ፡ ረዳኢየ ፡ ወመድኀኒየ ።



ወዳጆንና ፡ ባልንጀራዎን ፡ ፲፰
ዘመዶቼንም ፡ ከመከራ ፡ የተነሣ ፡ ከእኔ ፡ አራቅህ ።

መዝሙር ፡ ፹፰ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

አቤቱ ፡ ምሕረትህን ፡ ለዘላለም ፡ እዘምራለሁ ፡ ፩
እውነትህንም ፡ በአፌ ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ እናገራለሁ ።
አንተ ፡ ምሕረት ፡ ለዘላለም ፡ ይመሠረታል ፡ ብለሃልና ፡ ፪
እውነትህም ፡ በሰማይ ፡ ይጸናል ።
ከመረጥሁት ፡ ጋር ፡ ቃል፡ ኪዳኔን ፡ አደረግሁ ፡ ፫
ለባሪያዬም ፡ ለዳዊት ፡ ማልሁ ፡
ዘርህን ፡ ለዘላለም ፡ አዘጋጃለሁ ፡ ፬
ዙፋንህንም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ እመሠርታለሁ ።
አቤቱ ፡ ሰማያት ፡ ተአምራትህን ፡ ፭
እውነትህንም፡ ደግሞ፡ በቅዱሳን፡ ማኅበር፡ያመሰግናሉ ።
እግዚአብሔርን፡ በሰማይ፡ የሚተካከለው፡ ማን፡ነው ? ፮
ከአማልክትስ፡ልጆች፡እግዚአብሔርን ማን፡ይመስለዋል?
በቅዱሳን ፡ ምክር ፡ እግዚአብሔር ፡ ክቡር ፡ ነው ፡ ፯
በዙሪያው ፡ ባሉት ፡ ሁሉ፡ ላይ ፡ ታላቅና፡ግሩም ፡ ነው ።
አቤቱ፡የሠራዊት፡አምላክ፡ እንደ፡አንተ፡ ያለ፡ማን፡ነው ? ፰
አቤቱ ፡ አንተ ፡ ብርቱ ፡ ነህ ፡ እውነትህም ፡ ይከብሃል ።
የባሕርን ፡ ኃይል ፡ አንተ ፡ ትገዛለህ ፡ ፱
የሞገዱንም ፡ መናወጥ ፡ አንተ ፡ ዝም ፡ ታሰኛዋለህ ።
አንተ ፡ ትዕቢተኛውን ፡ እንደ፡ ተገደለ፡ አዋረድኸው ፡ ፲
በኃይልህም ፡ ክንድ ፡ ጠላቶችህን ፡ በተንሃቸው ።
ሰማያት ፡ የአንተ ፡ ናቸው፡ ምድርም፡ የአንተ ፡ ናት ፡ ፲፩
ዓለምንና ፡ ሞላውንም ፡ አንተ ፡ መሠረትህ ።
ሰሜንንና ፡ ደቡብን ፡ አንተ ፡ ፈጠርህ ፤ ፲፪
ታቦርና ፡ አርሞንዔምም ፡ በስምህ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፡

ክንድህ ፡ ከኀይልህ ፡ ጋር ፡ ነው ፡ ፲፫
እጅህ ፡ በረታች ፡ ቀኝህም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለች ።
የዙፋንህ ፡ መሠረት ፡ የጽድቅ ፡ ፍርድ ፡ ነው ፤ ፲፬
ምሕረትና ፡ እውነት ፡ በፊትህ ፡ ይሄዳሉ ።
የምስጋናን፡እልልታ፡የሚያውቅ፡ሕዝብ፡ምስጉን፡ነው ፡ ፲፭
አቤቱ ፡ በፊትህ ፡ ብርሃን ፡ ይሄዳሉ ።
በስምህ ፡ ቀኑን ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፡ ፲፮
በጽድቅህም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላሉ ።
የኃይላቸው ፡ መመኪያ ፡ አንተ ፡ ነህና ፡ ፲፯
በሞገስህም ፡ ኃይላችን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላልና ።
ረድኤታችን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ፲፰
ከንጉሣችንም ፡ ከእስራኤል ፡ ቅዱስ ፡ ነውና ።
በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ለልጆችህ ፡ በራእይ ፡ ተናገርህ ፡ ፲፱
እንዲህም ፡ አልህ ፡ ረድኤቴን ፡ በኃያል፡ ላይ፡አኖርሁ ፡
ከሕዝቤም ፡ የተመረጠውን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረግሁ ።
ባሪያዬን ፡ ዳዊትን ፡ አገኘሁት ፡ ፳
ቅዱስ ፡ ዘይቴንም ፡ ቀባሁት ።
እጄም ፡ ትረዳዋለች ፡ ፳፩
ክንዴም ፡ ታጸናዋለች ።
ጠላት ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ አይበረታም ፡ ፳፪
የዓመፃ ፡ ልጅም ፡ መከራ ፡ አያደርስበትም ።
ጠላቶቹን ፡ ከፊቱ ፡ አጠፋለሁ ፡ ፳፫
የሚጠሉትንም ፡ አዋርዳቸዋለሁ ።
እውነቴና ፡ ምሕረቴም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ነው ፡ ፳፬
በስሜም ፡ ሥልጣኑ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ።
እጁን ፡ በባሕር ፡ ላይ ፡ ፳፭
ቀኙንም ፡ በወንዞች ፡ ላይ ፡ አኖራለሁ ።
እርሱ ፡ አባቴና ፡ አምላኬ ፡ ፳፮
የመድኃኒቴም ፡ መጠጊያ ፡ አንተ ፡ ነህ ፡ ይላል ።

፳፯ ወአንሂ ፡ በኵርየ ፡ እሬስዮ ።
ወልዑል ፡ ውእቱ ፡ እምነገሥተ ፡ ምድር ።
፳፰ ወለዓለም ፡ አዐቅብ ፡ ሎቱ ፡ ሣህልየ ።
ወምእመን ፡ ውእቱ ፡ ለኪዳንየ ።
፳፱ ወእሬሲ ፡ ዘርዖ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ።
ወመንበሮሂ ፡ ከመ ፡ መዋዕለ ፡ ሰማይ ።
፴ ወእመሰ ፡ ኀደጉ ፡ ደቂቁ ፡ ሕግየ ። ወኢሖሩ፡በኵነኔየ ።
ወእመሂ ፡ አርኰሱ ፡ ሥርዐትየ ።
፴፩ ወኢዐቀቡ ፡ ትእዛዝየ ።
፴፪ እሐውጾሙ ፡ በበትር ፡ ለኀጢአቶሙ ።
ወበመቅሠፍት ፡ ለአበሳሆሙ ።
፴፫ ወሣህልየሰ ፡ ኢይከልእ ፡ እምኔሆሙ ።
ወኢይዔምፅ ፡ በጽድቅየ ።
፴፬ ወኢያረኵስ ፡ ኪዳንየ ።
ወኢይሔሱ ፡ ዘወፅአ ፡ እምአፉየ ።
ምዕረ ፡ መሐልኩ ፡ በቅዱስየ ።
፴፭ ከመ ፡ ለዳዊት ፡ ኢይሔስዎ ።
፴፮ ወዘርዑሂ ፡ ለዓለም ፡ ይሄሉ ።
ወመንበሩሂ ፡ ከመ ፡ ፀሐይ ፡ በቅድሜየ ።
፴፯ ወሥሩዕ ፡ ከመ ፡ ወርኅ ፡ ለዓለም ።
ወስምዑሂ ፡ ምእመን ፡ በሰማይ ።
፴፰ አንተሰ ፡ መነንከ ፡ ወገደፍከ ።
ወአናሕሰይከ ፡ ለመሲሕከ ።
፴፱ ወሜጥከ ፡ ሥርዐቶ ፡ ለገብርከ ።
ወአርኰስከ ፡ ውስተ ፡ ምድር ፡ መቅደሶ ።
፵ ወነሠትከ ፡ ኵሎ ፡ ጥቅሞ ።
ወረሰይከ ፡ አጽዋኒሁ ፡ መፍርሀ ።
፵፩ ወተማሠጠ ፡ ኵሉ ፡ ኀላፌ ፡ ፍኖት ።
፵፪ ወኮነ ፡ ጽዕለተ ፡ ለጎሩ ፡ ወአልዐልከ ፡ የማነ ፡ ፀሩ ።
ወአስተፍሣሕከ ፡ ኵሎ ፡ ጸላእቶ ።
፵፫ ወሜጥከ ፡ ረድኤተ ፡ ኲናቱ ።
፵፬ ወኢተወከፍከ ፡ በውስተ፡ጸብእ።ወሰዐርከ፡እምንጽሑ።
ወነፃኅከ ፡ ውስተ ፡ ምድር ፡ መንበሮ ።
፵፭ ወአውኀድከ ፡ መዋዕለ ፡ መንበሩ ።
ወሦጥከ ፡ ላዕሌሁ ፡ ኀፍረተ ።
፵፮ እስከ ፡ ማእዜኑ ፡ እግዚኦ ፡ ትመይጥ ፡ ለግሙራ ።
ወይነድድ ፡ ከመ ፡ እሳት ፡ መዓትከ ።
፵፯ ተዘከር ፡ ምንት ፡ ውእቱ ፡ ኃይልየ ።
ቦኑ ፡ ለከንቱ ፡ ፈጠርኮ ፡ ለኵሉ ፡ዕጓለ ፡ እመሕያው።
፵፰ መኑ ፡ ሰብእ ፡ ዘየሐዩ ፡ ወኢይሬእያ ፡ ለሞት ።
ወመኑ ፡ ዘያድኅና ፡ ለነፍሱ ፡ እምእደ ፡ ሲኦል ።
አይቴ ፡ ውእቱ ፡ ዘትካት ፡ ሣህልከ ፡ እግዚኦ ።
፵፱ ዘመሐልከ ፡ ለዳዊት ፡ ገብርከ ፡ በጽድቅ ።
፶ ተዘከር ፡ እግዚኦ ፡ ዘጸዐልዎሙ ፡ ለአግብርቲከ ።
ዘተወከፍኩ ፡ በሕፅንየ ፡ ብዙኀ ፡ አሕዛበ ።
፶፩ ዘጸዐሉ ፡ ጸላእትከ፡ እግዚኦ፡ ወጸዐሉ፡እብሬተ፡መሲሕከ
፶፪ ይትባረክ፡እግዚአብሔር ፡ ለዓለም ፡ ለይኩን፡ለይኩን ።

መዝሙር ፡ ፹፱ ።

ጸሎቱ ለሙሴ ብእሴ እግዚአብሔር በእንተ ትሩፋን ።

፩ እግዚኦ ፡ ፀወነ ፡ ኮንከነ ፡ ለትውልደ ፡ ትውልድ ።
፪ ዘእንበለ ፡ ይቁም፡አድባር፡ወይትፈጠር፡ዓለም፡ወምድር
እምቅድመ ፡ ዓለም ፡ ወእስከ ፡ ለዓለም፡አንተ ፡ ከመ።
፫ ኢትሚጦ ፡ ለሰብእ ፡ ለኀሳር ።
ወትቤ ፡ ተመየጡ ፡ ደቂቀ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ።



እኔም ፡ ደግሞ ፡ በኵሬ ፡ አደርገዋለሁ ፡ ፳፯
ከምድር ፡ ነገሥታትም ፡ ሁሉ ፡ ከፍ ፡ ይላል ።
ለዘላለምም ፡ ምሕረቴን ፡ ለእርሱ ፡ እጠብቃለሁ ፡ ፳፰
ኪዳኔም ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ የታመነ ፡ ነው ።
ዘሩንም ፡ ለዓለምና ፡ ለዘላለም ፡ አበዛለሁ ፡ ፳፱
ዙፋኑንም ፡ እንደ፡ሰማይ ፡ ዘመን ፡ አደርጋለሁ ።
ልጆቹ ፡ ግን ፡ ሕጌን ፡ ቢተዉ ፡ ፴
በፍርዴም ፡ ባይሄዱ ።
ሥርዓቴንም፡ ቢያረክሱ ፡ ፴፩
ትእዛዜንም ፡ ባይጠብቁ ።
ኃጢአታቸውን ፡ በበትር ፡ ፴፪
በደላቸውንም ፡ በመቅሠፍት ፡ እጐበኛታለሁ ።
ምሕረቴን ፡ ግን ፡ ከእርሱ ፡ አላርቅም ፡ ፴፫
በእውነቴም ፡ አላመነታም ።
ኪዳኔንም ፡ አላረክስም ፡ ፴፬
ከከንፈሬም ፡ የወጣውን ፡ አልለውጥም ።
ዳዊትን ፡ እንዳልዋሸው ፡ ፴፭
አንድ ፡ ጊዜ ፡ በቅዱስነቴ ፡ ማልሁ ።
ዘሩ ፡ ለዘላለም ፡ ይበዛል ፡ ፴፮
ዙፋኑም ፡ በፊቴ ፡ እንደ ፡ ፀሐይ ፡ ይኖራል ።
ለዘላለም ፡ እንደ ፡ ጨረቃ ፡ ይጸናል ፡ ፴፯
ምስክርነቱ ፡ በሰማይ ፡ የታመነ ፡ ነው ።
አንተ ፡ ግን ፡ ናቅኸው ፡ ፴፰
መሲሕህንም ፡ ጣልኸው ።
የባሪያህንም ፡ ኪዳን ፡ አፈረስህ ፡ ፴፱
መቅደሱንም ፡ በምድር ፡ አረከስህ ።
ቅጥሩን ፡ ሁሉ ፡ ጣልህ ፡ ፵
አምባዎቹንም ፡ አጠፋህ ።
መንገድ ፡ አላፊም ፡ ሁሉ ፡ ተናጠቀው ፡ ፵፩
ለጎረቤቶቹም ፡ መሰደቢያ ፡ ሆነ ።

የጠላቶቹንም ፡ ቀኝ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረግህ ፡ ፵፪
ጠላቶቹንም ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ አሰኘህ ።
የሰይፉንም ፡ ረድኤት ፡ መለስህ ፡ ፵፫
በሰልፍም ፡ ውስጥ ፡ አልደገፍኸውም ።
ከንጽሕናውም ፡ ሻርከው ፡ ፵፬
ዙፋኑንም ፡ በምድር ፡ ጣልህ ።
የዙፋኑንም ፡ ዘመን ፡ አሳነስህ ፡ ፵፭
በእፍረትም ፡ ሸፈንኸው ።
አቤቱ፡ እስከ፡ መቼ፡ ለዘላለም፡ ፊትህን፡ ትመልሳለህ ፡? ፵፮
እስከ ፡ መቼስ ፡ ቍጣህ ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ ይነዳል ። ?
ችሎታዬ ፡ እስከምን ፡ እደሆነ ፡ አስብ ፡ ፵፯
በውኑ ፡ የሰውን ፡ ልጅ፡ሁሉ ፡ ለከንቱ ፡ ፈጠርኸውን ?
ሕያው፡ ሆኖ፡ የሚኖር፡ ሞትንስ፡ የማያይ ፡ ማን ፡ ነው ? ፵፰
ነፍሱንስ ፡ ከሲኦል ፡ እጅ ፡ የሚያድን ፡ ማን ፡ ነው ። ?
ለዳዊት ፡ በእውነት ፡ የማልህ ፡ ፵፱
አቤቱ ፡ የቀድሞ ፡ ምሕረትህ ፡ ወዴት ፡ ነው ። ?
አቤቱ ፡ የባሮችህን ፡ ስድብ ፡ ፶
በብብቴ ፡ ብዙ ፡ አሕዛብን ፡ የተቀበልሁትን ።
አቤቱ ፡ ጠላቶች ፡ የሰደቡትን ፡ ፶፩
የመሲህን ፡ ዘመን ፡ የሰደቡትን ፡ አስብ ።
እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ ይባረክ ፡ ይሁን ፡ ይሁን ።

መዝሙር ፡ ፹፱ ።

ስለ ትሩፋን ና ፡

ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ባለሟል ፡ ስለ ፡ ሙሴ ፡ ጸሎት ።

አቤቱ ፡ አንተ፡ ለትውልድ፡ ሁሉ፡ መጠጊያ፡ ሆንህልን ። ፩
ተራሮች ፡ ሳይፈጠሩ ፡ ምድርም፡ ዓለምም፡ሳይመሠረቱ ፡ ፪
ከዘላለም ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ድረስ ፡ አንተ ፡ ነህ ።
ሰውን ፡ ወደ ፡ ኀሳር ፡ አትመልስም ፡ ፫
የሰው ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፡ ተመለሱ ፡ ትላለህ ።

፬ እስመ ፡ ዐሠርቱ ፡ ምእት ፡ ዓመት ።
በቅድሜከ ፡ ከመ ፡ ዕለት ፡ እንተ ፡ ትማልም፡ኀለፈት።
፭ ወሰዓተ ፡ ሌሊት ፡ ምንን ፡ ዓመታት ፡ በቅድሜከ ።
በጽባሕ ፡ ከመ ፡ ሣዕር ፡ የኀልፍ ።
፮ በጽባሕ ፡ ይሠርጽ ፡ ወየኀልፍ ።
ወሠርከሰ ፡ ይወድቅ ፡ የቢስ ፡ ወእንጺዎ ።
፯ እስመ ፡ ኀለቅነ ፡ በመዓትከ ።
ወደንገፅነ ፡ በመቅሠፍትከ ።
፰ ወሤምከ ፡ ኀጢአተነ ፡ ቅድሜከ ።
ወዓለምነሂ ፡ ውስተ ፡ ብርሃነ ፡ ገጽከ ።
፱ እስመ ፡ ኀልቁ ፡ ኵሉ ፡ መዋዕሊነ ።
ወኀለቅነ ፡ በመቅሠፍትከ ።
ወዓመቲነኒ ፡ ከመ ፡ ሣሬት ፡ ይከውና ።
፲ ወመዋዕለ ፡ ዓመቲነኒ ፡ ሰብዓ ፡ ክራማት ።
እመሰ ፡ በዝኅ ፡ ሰማንያ ፡ ዓም ።
ወፈድፋዶንሰ ፡ እምኤላ ፡ ፃማ ፡ ወሕማም ።
እስመ ፡ ኀለፈት ፡ የዋሀት ፡ እምኔነ ፡ ወተገሠጽነ ።
፲፩ መኑ ፡ የአምር ፡ ኀይለ ፡ መቅሠፍትከ ።
እምግርማ ፡ መዓትከ ፡ ኀልቊ ።
፲፪ ከመዝ ፡ አርኢ ፡ የማንከ ፡ ለምሁራነ ፡ ልብ ፡ በጥበብ ።
፲፫ ተመየጥ ፡ እግዚኦ ፡ እስከ ፡ ማእዜኑ ።
ወተናበብ ፡ በእንተ ፡ አግብርቲከ ።
፲፬ እስመ ፡ ጸገብነ ፡ በጽባሕ ፡ ምሕረተከ ።
ተፈሣሕነ ፡ ወተሐሠይነ ፡ በኵሉ ፡ መዋዕሊነ ።
፲፭ ወተፈሣሕነ ፡ ህየንተ ፡ መዋዕል ፡ ዘአሕመምከነ ።
ወህየንተ ፡ ዓመት ፡ እንተ ፡ ርኢናሃ ፡ ለእኪት ።
፲፮ ርኢ ፡ ላዕለ ፡ አግብርቲከ ፡ ወላዕለ ፡ ተግባርከ፡እግዚኦ።
ወምርሆሙ ፡ ለደቂቆሙ ።
፲፯ ለይኩን፡ ብርሃኑ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አምላክነ፡ ላዕሌነ።
ወይሠርሕ ፡ ለነ ፡ ተግባረ ፡ እደዊነ ።

መዝሙር ፡ ፺ ።

በእንተ ሕዝቅያስ ።

፩ ዘየኀድር ፡ በረድኤተ ፡ ልዑል ።
ወይነብር ፡ ውስተ ፡ ጽላሎቱ ፡ ለአምላከ ፡ ሰማይ ።
፪ ይብሎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ምስካይየ ፡ ወፀወንየ ፡ አንተ
አምላኪየ ፡ ወረዳኢየ ፡ ወእትዌከል ፡ ቦቱ ።
፫ እስመ ፡ ውእቱ ፡ይባልሐኒ ፡ እመሥገርት ፡ ነዓዊት ።
፬ ወእምነገር ፡ መደንግፅ ። ይጼልለከ ፡ በገበዋቲሁ ።
ወትትዌከል፡ በታሕተ ፡ ክነፊሁ ።
ጽድቅ ፡ በወልታ ፡ የዐውደከ ።
፭ ወኢትፈርህ ፡ እምግርማ ፡ ሌሊት ።
እምሐጽ ፡ ዘይሠርር ፡ በመዓልት ።
፮ እምግብር ፡ ዘየሐውር ፡ በጽልመት ።
እምድድቅ ፡ ወእምጋኔነ ፡ ቀትር ።
፯ ይወድቁ ፡ በገቦከ ፡ ዐሠርቱ ፡ ምእት ።
አእላፍ ፡ በየማንከ ፡ ወኀቤከሰ ፡ ኢይቀርቡ ።
፰ ወባሕቱ ፡ ትሬኢ ፡ በአዕይንቲከ ።
ወትሬኢ ፡ ፍዳሆሙ ፡ ለኃጥአን ።
፱ እስመ ፡ አንተ ፡ እግዚኦ ፡ ተስፋየ ።
ልዑለ ፡ ረሰይከ ፡ ፀወንከ ።
፲ ኢይቀርብ ፡ እኩይ ፡ ኀቤከ ።
ወኢይበውእ ፡ መቅሠፍት ፡ ቤተከ ።
እስመ ፡ ለመላእክቲሁ ፡ ይኤዝዞሙ ፡ በእንቲአከ ።
፲፩ ከመ ፡ ይዕቀቡከ ፡ በኵሉ ፡ ፍናዊከ ።
ወበእደዊሆሙ ፡ ያነሥኡከ ።
፲፪ ከመ ፡ ኢትትዐቀፍ ፡ በእብን ፡ እግርከ ።



ሺህ፡ዓመት፡በፊትህ፡እንደ፡አለፈች፡እንደ፡ ትናንት፡ቀን ፡ ፬
እንደ ፡ ሌሊትም ፡ ትጋት ፡ ነውና ። ፭
ዘመኖች ፡ የተናቁ ፡ ይሆናሉ ።
በማለዳም ፡ እንደ ፡ ሣር ፡ ያልፋል ።
ማልዶ ፡ ያብባል ፡ ያልፋልም ፡ ፮
በሠርክም ፡ ጠውልጎና ፡ ደርቆ ፡ ይወድቃል ።
እኛ ፡ በቍጣህ ፡ አልቀናልና ፡ ፯
በመዓትህም ፡ ደንግጠናልና ።
የተሰወረውን ፡ ኃጢአታችንን ፡ በፊትህ ፡ ብርሃን ፡ ፰
በደላችንንም ፡ በፊትህ ፡ አስቀመጥህ ።
ዘመናችን ፡ ሁሉ ፡ አልፎአልና ፡ ፱
እኛም ፡ በመዓትህ ፡ አልቀናል ።
ዘመኖቻችንም ፡ እንደ ፡ ሸረሪት ፡ ድር ፡ ይሆናሉ ።
የዘመኖቻችንም ፡ ዕድሜ ፡ ሰባ ፡ ዓመት ፡ ፲
ቢበረታም ፡ ሰማንያ ፡ ዓመት ፡ ነው ።
ከዚያ ፡ ቢበዛ ፡ ግን ፡ ድካምና ፡ መከራ ፡ ነው ።
ከእኛ ፡ ቶሎ ፡ ያልፋልና ፡ እኛም ፡ ተገሥጸናልና ።
የቍጣህን ፡ ጽናት ፡ ማን ፡ ያውቃል ? ፲፩
ከቍጣህ ፡ ግርማ ፡ የተነሣ ፡ አለቁ ።
በልብ ፡ ጥበብን ፡ እንድንማር ፡ ፲፪
ቀኝህን ፡ እንዲህ ፡ አስታውቀን ።
አቤቱ ፡ ተመለስ ፡ እስከ ፡ መቼስ ፡ ነው ? ፲፫
ስለ ፡ ባሮችህም ፡ ተከራከር ።
በማለዳ ፡ ምሕረትህን ፡ እንጠግባለን ፡ ፲፬
በዘመናችን፡ሁሉ፡ደስ፡ይለናል፡ ሐሤትም፡ እናደርጋለን ።
መከራ ፡ በአሳየኸኝ ፡ ዘመን ፡ ፈንታ ፡ ፲፭
ክፉም ፡ በአየንባቸው ፡ ዘመኖች ፡ ፈንታ ፡ ደስ ፡ ይለናል ።
ባሮችህንና ፡ ሥራህን ፡ እይ ፡ ፲፮
ልጆችህንም ፡ ምራ ።
የአምላካችን፡የእግዚአብሔር፡ብርሃን፡በላያችን፡ይሁን፡ ፲፯
የእጆቻችንንም ፡ ሥራ ፡ በላያችን ፡ አቅና ።

መዝሙር ፡ ፺ ።

ስለ ፡ ሕዝቅያስ ።

በልዑል ፡ መጠጊያ ፡ የሚኖር ፡ ፩
ሁሉን ፡ በሚችል ፡ አምላክ ፡ ጥላ፡ውስጥ ፡ ያድራል ።
እግዚአብሔርን ፡ አንተ ፡ መታመኛዬ ፡ ነህ ፡ እለዋለሁ ፡ ፪
አምላኬና ፡ መሸሸጊያዬ ፡ ነው ፡ በርሱም፡ እታመናለሁ ።
እርሱ ፡ ከአዳኝ ፡ ወጥመድ ፡ ፫
ከሚያስደነግጥም ፡ ነገር ፡ ያድንሃልና ።
በላባዎቹ ፡ ይጋርድሃል ፡ ፬
በክንፎቹም ፡ ጥላ ፡ ትጠለላለህ ።
እውነት ፡ እንደ ፡ ጋሻ ፡ ይከብሃል ።
ከሌሊት ፡ ግርማ ፡ ፭
በቀን ፡ ከሚበር ፡ ፍላፃ ።
በጨለማ ፡ ከሚሄድ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ፮
ከአደጋና ፡ ከቀትር ፡ ጋኔን ፡ አትፈራም ።
በአጠገብህ ፡ ሺህ፡ በቀኝህም፡ ዓሥር፡ ሺህ፡ ይወድቃሉ፡ ፯
ወደ ፡ አንተ ፡ ግን ፡ አይቀርቡም ።
በዓይኖችህ ፡ ብቻ ፡ ትመለከታለህ ፡ ፰
የኃጥአንንም ፡ ብድራት ፡ ታያለህ ።
አቤቱ ፡ አንተ ፡ ተስፋዬ ፡ ነህና ፡ ፱
ልዑልን ፡ መጠጊያህ ፡ አደረግህ ።
ክፉ ፡ ነገር ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ አይቀርብም ፡ ፲
መቅሠፍትም ፡ ወደ ፡ ቤትህ ፡ አይገባም ።
በመንገድህ ፡ ሁሉ ፡ ይጠብቁህ ፡ ዘንድ ፡ ፲፩
መላእክቱን ፡ ስለ ፡ አንተ ፡ ያዛቸዋልና ።
እግርህም ፡ በድንጋይ ፡ እንዳትሰናከል ፡ ፲፪
በእጆቻቸው ፡ ያነሡሃል ።

፲፫ ላዕለ ፡ ተኵላ ፡ ወከይሲ ፡ ትጼዓን ።
ወትከይድ ፡ አንበሳ ፡ ወከይሴ ።
፲፬ እስመ ፡ ብየ ፡ ተወከለ ፡ አድኅኖ ።
ወእከድኖ ፡ እስመ ፡ አእመረ ፡ስምየ ።
፲፭ ይጼውዐኒ ፡ ወእሰጠዎ ።
ሀሎኩ ፡ ምስሌሁ ፡ አመ ፡ ምንዳቤሁ ።
ድኅኖ ፡ ወእሴብሖ ።
፲፮ ለነዋኅ ፡ መዐዋል ፡ አጸግቦ ።
ወአርእዮ ፡ አድኅኖትየ ።

መዝሙር ፡ ፺፩ ።

በእንተ ሕዝቅያስ ።

፩ ይኄይስ ፡ ተአምኖ ፡ በእግዚአብሔር ።
ወዘምሮ ፡ ለስምከ ፡ ልዑል ።
፪ ወንጊር ፡ በጽባሕ ፡ ምሕረተከ ። ወጽድቀከኒ፡በሌሊት።
፫ በዘዐሠርቱ ፡ አውታሪሁ፡መዝሙረ፡ማኅሌት፡ወመሰንቆ
፬ እስመ ፡ አስተፍሣሕከኒ ፡ እግዚኦ ፡ በምግባሪከ ።
ወእትሐሠይ ፡ በግብረ ፡ እደዊከ ።
፭ ጥቀ ፡ ዐቢይ ፡ ግብርከ ፡ እግዚኦ ።
፮ ወፈድፋደ ፡ዕሙቅ፡ ኅሊናከ።ብእሲ፡አብድ፡ኢየአምር።
ወዘአልቦ ፡ ልብ ፡ ኢይሌብዎ ፡ ለዝንቱ ።
፯ ሶበ ፡ ይበቍሉ ፡ ኃጥአን ፡ ከመ ፡ ሣዕር ።
ወይሠርፁ ፡ ኵሎሙ ፡ ገበርተ ፡ ዓመፃ ።
ከመ ፡ ይሠረዉ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ።
፰ አንተሰ ፡ ልዑል ፡ ለዓለም ፡ እግዚኦ ።
፱ እስመ ፡ ናሁ ፡ ጸላእትከ ፡ ይትሀጎሉ ።
ወይዘረዉ ፡ ኵሎሙ ፡ ገበርተ ፡ ዐመፃ ።
፲ ወይትሌዐል ፡ ቀርንየ ፡ ከመ ፡ ዘአሐዱ ፡ ቀርኑ ።
ወይጠልል ፡ በቅብዕ ፡ ሢበትየ ።
፲፩ ወርእየት ፡ ዐይንየ ፡ በጸላእትየ ።
ወሰምዐት እዝንየ ዲበሆሙ ለእኩያን እለ ቆሙ ላዕሌየ ።
፲፪ ጻድቅሰ ፡ ከመ ፡ በቀልት ፡ ይፈሪ ።
ወይበዝኅ ፡ ከመ ፡ ዘግባ ፡ ዘሊባኖስ ።
፲፫ ትኩላን ፡ እሙንቱ ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ እግዚአብሔር ።
ወይበቍሉ ፡ ውስተ ፡ ዐጸዱ ፡ ለአምላክነ ።
፲፬ ውእተ ፡ አሚረ ፡ ይበዝኁ ፡ በርሥአን ፡ ጥሉል ።
ወይከውኑ ፡ ዕሩፋነ ።
፲፭ ወይነግሩ ፡ ከመ፡ጻድቅ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክነ ።
ወአልቦ ፡ ዐመፃ ፡ በኀቤሁ ።

መዝሙር ፡ ፺፪ ።

በእንተ ትሩፋን ።

፩ እግዚአብሔር ፡ ነግሠ ፡ ስብሐቲሁ ፡ ለብሰ ።
ለብሰ ፡ እግዚአብሔር ፡ ኀይሎ ፡ ወቀነተ ።
ወአጽንዓ ፡ ለዓለም ፡ ከመ ፡ ኢታንቀለቅል ።
፪ ድልው ፡ መንበርከ ፡ እግዚኦ ።
እምትካት ፡ ወእስከ ፡ ለዓለም ፡ አንተ ፡ ከመ ።
፫ አልዐሉ ፡ አፍላግ ፡ እግዚኦ ።
አልዐሉ ፡ አፍላግ ፡ ቃላቲሆሙ ።
፬ እምቃለ ፡ማያት ፡ ብዙኅ ፡ መንክር ፡ ተላህያ ፡ ለባሕር።
መንክርሰ ፡ እግዚአብሔር ፡ በአርያም ።
፭ ስምዐ ፡ ዚአከ ፡ እሙን ፡ ፈድፋደ ።
ለቤትከ ፡ ይደሉ ፡ ስብሐት ፡ እግዚኦ፡ለነዋኅ፡መዋዕል።



በተኵላና ፡ በእባብ ፡ ላይ ፡ ትጫማለህ ፡ ፲፫
ዘንዶውንና ፡ አንበሳውንም ፡ ትረግጣለህ ።
በእኔ ፡ ተማምኖአልና ፡ አስጥለዋለሁ ፡ ፲፬
ስሜንም ፡ አውቋልና ፡ እጋርደዋለሁ ።
ይጠራኛል ፡ እመልስለትማለሁ ፡ ፲፭
በመከራውም ፡ ጊዜ ፡ ከእርሱ ፡ ጋራ ፡ እሆናለሁ ።
አድነዋለሁ ፡ አከብረውማለሁ ።
ረጅም ፡ ዕድሜ ፡ አስጠግበዋለሁ ፡ ፲፮
ማዳኔንም ፡ አሳየዋለሁ ።

መዝሙር ፡ ፺፩ ።

ስለ ፡ ሕዝቅያስ ።

እግዚአብሔርን ፡ ማመስገን ፡ መልካም ፡ ነው ። ፩
ልዑል፡ሆይ፡ለስምህም፡ዝማሬ፡ማቅረብ፡መልካም፡ነው።
ዐሥር ፡ አውታር ፡ ባለው ፡ በበገና ፡ ፪
ከምሥጋና ፡ ጋራም ፡ በመሰንቆ ፡
መዘመር ፡ ድንቅ ፡ ነው ። ፫
በሌሊትም ፡ በማለዳ ፡ ምሕረትን ፡
እውነትህን ፡ ማውራት ፡ የተሻለ ፡ ነው ።
አቤቱ ፡ በሥራህ ፡ ደስ ፡ አሰኝተኸኛልና ፡ ፬
በእጅህም ፡ ሥራ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ።
አቤቱ ፡ ሥራህ ፡ እጅግ ፡ ታላቅ ፡ ነው ፡ ፭
አሳብህም ፡ እጅግ ፡ ጥልቅ ፡ ነው ።
ሰነፍ ፡ ሰው ፡ አያውቅም ፡ ፮
ልብ ፡ የሌለውም ፡ ይኸን ፡ አያስተውለውም ።
ኀጢአተኞች ፡ እንደ ፡ ሣር ፡ ሲበቅሉ ፡ ፯
ዓመፃ ፡ የሚያደርጉ ፡ ሁሉ ፡ ሲለመልሙ ።
ለዘላለም ፡ ዓለም ፡ እንዲጠፉ ፡ ነው ።
አቤቱ ፡ አንተ ፡ ግን ፡ ለዘላለም ፡ ልዑል ፡ ነህ ። ፰
አቤቱ ፡ እነሆ ፡ ጠላቶችህ ፡ ይጠፋሉና ፡ ፱
ዓመፃንም ፡ የሚሠሩ ፡ ሁሉ ፡ ይበተናሉና ።
ቀንዴ ፡ አንድ ፡ ቀንድ ፡ እንዳለው ፡ ከፍ፡ ከፍ ፡ ይላል ፡ ፲
ሽምግልናዬም ፡ በዘይት ፡ ይለመልማል ።
ዓይኔም ፡ ጠላቶቼን ፡ አየች ፡ ፲፩
ጆሮዬም፡ በእኔ፡ላይ፡ በቆሙ፡ በክፉዎች፡ ላይ፡ ሰማች ።
ጻድቅ ፡ እንደ ፡ ዘንባባ ፡ ያፈራል ፡ ፲፪
እንደ ፡ ሊባኖስ ፡ ዝግባም ፡ ያድጋል ።
በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ ተተክለዋል ፡ ፲፫
በአምላካችንም ፡ አደባበይ ፡ ውስጥ ፡ ይበቅላሉ ።
ያን ፡ ጊዜ ፡ በለመለመ ፡ ሽምግልና ፡ ያፈራሉ ፡ ፲፬
ደስተኞችም ፡ ሆነው ፡ ይኖራሉ ።
አምላኬ ፡ እግዚአብሔር ፡እውነተኛ ፡ እንደሆነ ፡ ፲፭
ይነግራሉ ፡
በእርሱም ፡ ዘንድ ፡ ዓመፃ ፡ የለም ።

መዝሙር ፡ ፺፪ ።

ስለ ትሩፋን ።

እግዚአብሔር ፡ ነገሠ ፡ ክብርንም ፡ ለበሰ ፡ ፩
እግዚአብሔር ፡ ኀይልን ፡ ለበሰ ፡ ታጠቀም ።
ዓለምን ፡ እንዳትናወጥ ፡ አጸናት ።
ዙፋንህ ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ የተዘጋጀ ፡ ነው ፡ ፪
አንተም ፡ ከዘላለም ፡ እስከዘላለም ፡ ነህ ።
አቤቱ ፡ ወንዞች ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረጉ ፡ ፫
ወንዞች ፡ ቃሎቻቸውን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረጉ ።
ከብዙ ፡ ውኆች ፡ ድምፅ ፡ ፬
ከባሕርም ፡ ታላቅ ፡ ሞገድ ፡ ይልቅ ፡
እግዚአብሔር ፡ በከፍታው ፡ ግሩም ፡ ነው ።
ምስክርነትህ ፡ እጅግ ፡ የታመነ ፡ ነው ፡ ፭
አቤቱ፡እስከ፡ዘላለሙ፡ድረስ፡ለቤትህ፡ቅድስና፡ይገባል።

መዝሙር ፡ ፺፫ ።

በአንተ ትሩፋን ።

፩ እግዚአብሔር ፡ እግዚእ ፡ መስተበቅል ።
እግዚአብሔር ፡ መስተበቅል ፡ ገሃደ ።
፪ ተለዐል ፡ ዘይኴንና ፡ ለምድር ።
ፍድዮመ ፡ ፍዳሆሙ ፡ ለዕቡያን ።
፫ እስከ ፡ ማእዜኑ ፡ ኃጥአን ፡ እግዚአ ።
እስከ ፡ ማእዜኑ ፡ ይዜኀሩ ፡ ኃጥአን ።
፬ ይትዋሥኡ ፡ ወይነቡ ፡ ዐመፃ ።
ወይነቡ ፡ ኵሎሙ ፡ ገበርተ ፡ ዐመፃ ።
፭ ወአኅሰሩ ፡ ሕዝበከ ፡ እግዚኦ ፡ ወሣቀዩ ፡ ርስተከ ።
፮ ወቀተሉ ፡ ዕቤረ ፡ ወዕጓለ ፡ ማውታ ።
ወቀተሉ ፡ ፈላሴ ።
፯ ወይቤሉ ፡ ኢይሬኢ ፡ እግዚአብሔር ።
ወኢየአምር ፡ አምላከ ፡ ያዕቆብ ።
፰ ለብዉ ፡ አብዳን ፡ ሕዝብ፡አብዳንኬ ፡ ማእዜ ፡ ይጠቡ።
፱ ዘተከላሁ ፡ ለእዝን ፡ ኢይሰምዕኑ ።
ወዘፈጠራሁ ፡ ለዐይን ፡ ኢይሬኢኑ ።
፲ ዘይጌሥጾሙ ፡ ለአሕዛብ ፡ ኢይዛለፍኑ ።
ዘይሜህሮሙ ፡ ለሰብእ ፡ ጥበበ ።
፲፩ እግዚአብሔር ፡ የአምር ፡ ኅሊናሆሙ ፡ ለጠቢባን ፡
ከመ ፡ ከንቱ ፡ ውእቱ ።
፲፪ ብፁዕ ፡ ብእሲ ፡ ዘአንተ ፡ ገሠጽኮ ፡ እግዚኦ ።
ወዘመሀርኮ ፡ ሕገከ ።
ከመ ፡ ይትገሃሥ ፡ እመዋዕለ ፡ እኩያት ።
፲፫ እስከ ፡ ይትከረይ ፡ ግብ ፡ ለኃጥአን ።
፲፬ እስመ ፡ ኢይገድፎሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሕዝቡ ።
ወኢየኀድጎሙ ፡ ለርስቱ ።

፲፭ እስከ ፡ ይገብእ ፡ ፍትሕ ፡ ለዘይጸድቅ ።
ወኵሎሙ ፡ ርቱዓነ ፡ ልብ ፡ እለ ፡ ኪያሃ ፡ በሙ ።
፲፮ መኑ ፡ ይትዋሥአኒ ፡ በእንተ ፡ እኩያት ።
ወመኑ ፡ ይትቃወመኒ ፡ በእንተ ፡ ገበርተ ፡ ዐመፃ ።
፲፯ ሶበ ፡ አኮ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዘረድአኒ ።
ሕቀ ፡ ከመ ፡ ዘእምኀደረት ፡ ነፍስየ ፡ ውስተ ፡ ሲኦል።
፲፰ ወሶበ፡እቤ፡ድኀፀ፡እገርየ። ምሕረትከ፡ እግዚኦ፡ ረድአኒ።
፲፱ እግዚኦ ፡ በከመ ፡ ብዝኀ ፡ ሕማማ ፡ ለልብየ ።
ናዝዞትከ ፡ አስተፍሥሐ ፡ ለነፍስየ ።
ወኢይትቃወመከ ፡ መንበረ ፡ ዐመፃ ።
፳ ዘይፈጥር ፡ ፃማ ፡ ዲበ ፡ ትእዛዝ ።
፳፩ ወይነዕዋ ፡ ለነፍሰ ፡ ጻድቅ፡ወይኴንኑ ፡ ደመ ፡ ንጹሐ ።
፳፪ ወኮነኒ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፀወንየ ።
አምላኪየ ፡ ወረድኤተ ፡ ተስፋየ ።
፳፫ ወይፈድዮሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ በከመ ፡ እከዮሙ ።
ወያጠፍኦሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክነ ።

መዝሙር ፡ ፺፬ ።

በአንተ ትሩፋን ።

፩ ንዑ ፡ ንትፈሣሕ ፡ በእግዚአብሔር ።
ወንየብብ ፡ ለአምላክነ ፡ ወመድኀኒነ ።
፪ ወንብጻሕ ፡ ቅድመ ፡ ገጹ ፡ በአሚን ።
ወበመዝሙር ፡ ንየብብ ፡ ሎቱ ።
፫ እስመ ፡ ዐቢይ ፡ ውእቱ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክነ ።
ወንጉሥ ፡ ዐቢይ ፡ ውእቱ ፡ ላዕለ ፡ ኵሉ ፡ አማልክት ።
፬ እስመ ፡ ኢይገድፎሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሕዝቡ ።
እስመ ፡ ውስተ ፡ እዴሁ ፡ ኵሉ ፡ አጽናፈ ፡ ምድር ።
አድባር ፡ ነዋኃት ፡ ዚአሁ ፡ ውእቱ ።



መዝሙር ፡ ፺፫ ።
ስለ ትሩፋን ።

እግዚአብሔር ፡ የበቀል ፡ አምላክ ፡ ነው ፡ ፩
የበቀል ፡ አምላክ ፡ ተገለጠ ።
የምድር ፡ ፈራጅ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ በል ፡ ፪
ለትዕቢተኞች ፡ ፍዳቸውን ፡ ክፈላቸው ።
አቤቱ ፡ ኀጢአተኞች ፡ እስከ ፡ መቼ ? ፫
ኀጢአተኞች ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ይኳደዳሉ ? ።
ይከራከራሉ ፡ ዓመፃንም ፡ ይናገራሉ ፡ ፬
ዓመፅንም ፡ የሚያደርጉ ፡ ሁሉ ፡ ይናገራሉ ።
አቤቱ ፡ ሕዝብህን ፡ አዋረዱ ፡ ፭
ርስትህንም ፡ አስቸገሩ ።
ባልቴቲቱንና ፡ ድሀ ፡ አደጉን ፡ ገደሉ ፡ ፮
ስደተኛውንም ፡ ገደሉ ።
እግዚአብሔር ፡ አያይም ፡ ፯
የያዕቆብም ፡ አምላክ ፡ አያስተውልም ፡ አሉ ።
የሕዝብ ፡ ደንቆሮዎች ፡ ሆይ ፡ አስተውሉ ፡ ፰
ሰነፎችማ ፡ መቼ ፡ ይጠበባሉ ?
ጆሮን ፡ የተከለው ፡ አይሰማምን ? ፱
ዓይንን ፡ የሠራው ፡ አያይምን ። ?
አሕዛብንስ ፡ የሚገሥጽ ፡ ፲
ለሰውም ፡ ዕውቀትን ፡ የሚያስተምር ፡ እርሱ ፡ አይዘልፍምን ፡ ?
የሰዎች ፡ አሳብ ፡ ከንቱ ፡ እንደሆነ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያውቃል ፡ ፲፩
ለኃጢአተኛ ፡ ጉድጓድ ፡ እስኪቆፈር ፡ ድረስ ፡ ፲፪
ከክፉዎች ፡ ዘመናት ፡ ይወገድ ፡ ዘንድ ።
አቤቱ ፡ አንተ ፡ የገሠጽኸው ፡ ፲፫
ሕግህንም ፡ ያስተማርኸው ፡ ሰው ፡ ምስጉን ፡ ነው ።
እግዚአብሔር ፡ ሕዝቡን ፡ አይጥልምና ፡ ፲፬
ርስቱንም ፡ አይተውምና ።

ፍርድ ፡ ወደ ፡ ጽድቅ ፡ እስኪመለስ ፡ ድረስ ፡ ፲፭
ልበ ፡ ቅኖችም ፡ ሁሉ ፡ ይከተሏታል ።
በክፉዎች ፡ ላይ ፡ ስለእኔ ፡ ማን ፡ ይቆማል ? ፲፮
ዓመፅንስ ፡ በሚያደርጉ ፡ ላይ ፡ ከእኔ ፡ ጋራ ፡ ማን ፡ ይከራከራል ።
እግዚአብሔር ፡ የረዳኝ ፡ ባይሆን ፡ ፲፯
ነፍሴ ፡ ለጥቂት ፡ ጊዜ ፡ በሲኦል ፡ በአደረች ፡ ነበር ።
እግሮቼ ፡ ተሰናከሉ ፡ ባልሁ ፡ ጊዜ ፡ ፲፰
አቤቱ ፡ ምሕረትህ ፡ ረዳኝ ።
አቤቱ ፡ ለልቤ ፡ እንደ ፡ መከራዋ ፡ ብዛት ፡ ፲፱
ማጽናናትህ ፡ ነፍሴን ፡ ደስ ፡ አሰኛት ።
በሕግ ፡ ላይ ፡ ዓመፅን ፡ የሚሠራ ፡ ፳
የዓመፅ ፡ ዙፋን ፡ ከአንተ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ይሆናልን ።
የጻድቅን ፡ ነፍስ ፡ ያድቡባታል ፡ ፳፩
በንጹሕ ፡ ደምም ፡ ይፈርዳሉ ።
እግዚአብሔር ፡ መጠጊያ ፡ ሆነኝ ፡ ፳፪
አምላኬ ፡ የተስፋዬም ፡ ረዳት ፡ ነው ።
እንደ ፡ ክፋታቸውም ፡ ፍዳቸውን ፡ ይከፍላቸዋል ፡ ፳፫
አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡ያጠፋቸዋል ።

መዝሙር ፡ ፺፬ ።
ስለ ትሩፋን ።

ኑ ፡ በእግዚአብሔር ፡ደስ ፡ ይበለን ። ፩
ለአምላክ ፡ ለመድኀኒታችን ፡ እልል ፡ እንበል ።
በምስጋና ፡ ወደፊቱ ፡ እንድረስ ፡ ፪
በዝማሬም ፡ ለርሱ ፡ እልል ፡ እንበል ።
እግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፡ አምላክ ፡ ነውና ፡ ፫
በአማልክትም ፡ ሁሉ፡ላይ ፡ ታላቅ ፡ ንጉሥ ፡ ነውና ።
እግዚአብሔር ፡ ሕዝቡን ፡ አይጥላቸውም ፡ ፬
የምድር ፡ ዳርቻዎችም ፡ በእጁ ፡ ውስጥ ፡ ናቸው ፡
የተራሮች ፡ ከፍታዎች ፡ የእርሱ ፡ ናቸው ።

፭ እስመ ፡ እንቲአሁ ፡ ይእቲ ፡ ባሕር፡ወውእቱ፡ፈጠራ ።
ወለየብስኒ ፡ እደዊሁ ፡ ገብራ ።
፮ ንዑ ፡ ንስግድ ፡ ወንግነይ ፡ ሎቱ ።
ወንብኪ ፡ ቅድመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዘውእቱ ፡ ፈጠረነ
፯ እስመ ፡ ውእቱ ፡ አምላክነ ።
ንሕነሰ ፡ ሕዝቡ ፡ ወአባግዐ ፡ መርዔቱ ።
ዮም ፡ እመ ፡ ሰማዕክሙ ፡ ቃሎ።ኢታጽንዑ፡ልበክሙ።
፰ ከመ ፡ አመ ፡ አምረርዎ ፡ በገዳም ።
፱ ወከመ ፡ አመ ፡ አመከርዎ።ዘአመከሩኒ ፡ አበዊክሙ ።
ፈተኑኒ ፡ ወርእዩ ፡ ምግባርየ ።
፲ አርብዓ ፡ ዓመተ ፡ ተቆጣዕክዋ ፡ ለይእቲ ፡ ትውልድ ።
ወእቤ ፡ ዘልፈ ፡ ይስሕት ፡ ልቦሙ ።
እሙንቱሰ ፡ ኢያእመሩ ፡ ፍናውየ ።
በከመ ፡ መሐልኩ ፡ በመዓትየ ።
፲፩ ከመ ፡ ኢይበውኡ ፡ ውስተ ፡ ዕረፍትየ ።

መዝሙር ፡ ፺፭ ።

በእንተ ትሩፋን ።

፩ ሰብሕዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስብሐተ ፡ ሐዲሰ ።
ሰብሕዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ኵላ ፡ ምድር ።
፪ ሰብሕዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ወባርኩ ፡ ለስሙ ።
ወተዘየነዉ ፡ እምዕለት ፡ ዕለተ ፡ አድኅኖቶ ።
፫ ወንግርዎሙ ፡ ለአሕዛብ ፡ ስብሐቲሁ ።
ወለኵሎሙ ፡ አሕዛብ ፡ ተአምሪሁ ።
፬ እስመ ፡ ዐቢይ እግዚአብሔር ፡ ወብዙኅ ፡ አኰቴቱ ።
ወግሩም ፡ ውእቱ ፡ ላዕለ ፡ ኵሉ ፡ አማልክት ።
፭ እስመ ፡ አማልክተ ፡ አሕዛብ ፡ አጋንንት ።
እግዚአብሔርሰ ፡ ሰማያተ ፡ ገብረ ፡
፮ አሚን ፡ ወሠናይት ፡ ቅድሜሁ ።
ቅድሳት ፡ ወዕበየ ፡ ስብሐት ፡ ውስተ ፡ መቅደሱ ።
፯ አምጽኡ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በሐውርተ ፡ አሕዛብ ።
አምጽኡ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ክብረ ፡ ወስብሐተ ።
፰ አምጽኡ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስብሐተ ፡ ለስሙ ።
ንሥኡ ፡ መሥዋዕተ ፡ ወባኡ ፡ ውስተ ፡ አዕጻዲሁ ።
፱ ስግዱ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በዐጸደ ፡ መቅደሱ ።
ታድለቀልቅ ፡ እምቅድመ ፡ ገጹ ፡ ለእግዚአብሔር ኵላ ፡ ምድር ።
፲ በልዎሙ ፡ ለአሕዛብ ፡ ከመ እግዚአብሔር ፡ ነግሠ ።
ወአጽንዓ ፡ ለዓለም ፡ ከመ ፡ ኢታንቀለቅል ።
ወይኴንኖሙ ፡ ለአሕዛብ ፡ በርትዕ ።
፲፩ ይትፌሣሑ ፡ ሰማያት ፡ ወትትሐሠይ ፡ ምድር ።
ወትትከወስ ፡ ባሕር ፡ በምልዓ ።
፲፪ ትትሐሠይ ፡ ገዳም ፡ ወኵሉ ፡ ዘውስቴታ ።
ውእተ ፡ አሚረ ፡ ይትፌሥሑ ፡ ኵሉ ፡ ዕፀወ ፡ ገዳም ።
እምቅድመ ፡ ገጹ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እስመ ፡ ይመጽእ
፲፫ ይመጽእ ፡ ወይኴንና ፡ ለምድር ።
ወይኴንና ፡ ለዓለም፡ በጽድቅ ። ወለአሕዛብኒ፡ በርትዕ።

መዝሙር ፡ ፺፮ ።

በእንተ ትሩፋን ።

፩ እግዚአብሔር ፡ ነግሠ ፡ ትትሐሠይ ፡ ምድር ።
፪ ወይትሐሠያ ፡ ደሰያት ፡ ብዙኃት ።
ደመና ፡ ወቆባር ፡ ዐውዱ ።
ፍትሕ ፡ ወርትዕ ፡ ተድላ ፡ መንበሩ ።
፫ እሳት ፡ የሐውር ፡ ቅድሜሁ ።
ወነድ ፡ የዐግቶሙ ፡ ለጸላእቱ ።
፬ አስተርአየ ፡ መባርቅቲሁ ፡ ለዓለም ።
ርእየት ፡ ወአድለቅለቀት ፡ ምድር ።



ባሕር ፡ የእርሱ ፡ ናት ፡ እርሱም ፡ ሠራት ፡ ፭
የብስንም ፡ እጆቹ ፡ ሠሩዋት ።
ኑ ፡ እንስገድ ፡ ለእርሱም ፡ እንገዛ ፡ ፮
የእርሱ፡በአደረገን፡በእግዚአብሔር ፊት፡እንንበርከክ ።
እርሱ ፡ አምላካችን ፡ ነውና ፡ ፯
እኛ ፡ የማሰማሪያው ፡ ሕዝብ ፡ የእጁም ፡ በጎች ፡ ነንና ።
በምድረ፡በዳ ፡እንደ፡ተፈታተኑት፡እንዳስቆጡት፡ጊዜ ፡ ፰
ዛሬ ፡ ድምፁን ፡ ብትሰሙ ፡ ልባችሁን ፡ አታጽኑ ።
የተፈታተኑኝ ፡ አባቶቻችሁ ፡ ፱
ፈተኑኝ ፡ ሥራዬንም ፡ አዩ ።
ያችን ፡ ትውልድ ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡ ተቆጥቻት ፡ ነበር ፡ ፲
ሁል ፡ ጊዜም ፡ ልባቸው ፡ ይስታል ።
እነርሱም ፡ መንገዴን ፡ አላወቁም ፡ አልሁ ።
ወደ ፡ ዕረፍቴም ፡ እንዳይገቡ ፡ በቍጣዬ ፡ ማልሁ ። ፲፩

መዝሙር ፡ ፺፭ ።

ስለ ትሩፋን ።

ለእግዚአብሔር ፡ አዲስ ፡ ምስጋናን ፡ አመስግኑ ፡ ፩
ምድር ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ።
እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ፡ ስሙንም ፡ ባርኩ ፡ ፪
ዕለት ፡ ዕለትም ፡ ማዳኑን ፡ አውሩ ።
ክብሩን ፡ ለአሕዛብ ፡ ፫
ተአምራቱንም ፡ ለወገኖች ፡ ሁሉ ፡ ንገሩ ።
እግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፡ ምስጋናውም ፡ ብዙ ፡ ነውና ፡ ፬
በአማልክትም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ የተፈራ ፡ ነውና ።
የአሕዛብ ፡ አማልክት ፡ ሁሉ ፡ አጋንንት ፡ ናቸው ፡ ፭
እግዚአብሔር ፡ግን ፡ ሰማያትን ፡ ሠራ ።
ምስጋናና ፡ ውበት ፡ በፊቱ ፡ ፮
ቅዱስነትና ፡ግርማ ፡ በመቅደሱ ፡ ውስጥ ፡ ናቸው ።
የአሕዛብ ፡ ወገኖች ለእግዚአብሔር ፡ አምጡ ፡ ፯
ክብርንና ፡ ምስጋናን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አምጡ ።
ለስሙ ፡ የሚገባ ፡ ክብርን ለእግዚአብሔር አምጡ ፡ ፰
ቍርባን ፡ ያዙ ፡ ወደ ፡ አደባባዮችም ፡ ግቡ ።
በቅድስናው ፡ ሥፍራ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስገዱ ፡ ፱
ምድር ፡ ሁሉ ፡ በርሱ ፡ ፊት ፡ ትነዋወጥ ።
ለአሕዛብ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነገሠ ፡ በሏቸው ፡ ፲
እንዳይናወጥም ፡ ዓለሙን ፡ እርሱ ፡ አጸናው ፤
ለአሕዛብም ፡ በቅንነት ፡ ይፈርዳል ።
ሰማያት፡ደስ፡ይበላቸው፡ምድርም፡ሐሤትን፡ታድርግ ፡ ፲፩
ባሕርና ፡ በእርሷ ፡ ያለ ፡ ሁሉ ፡ ይናወጡ ፡
በምድር ፡ ሊፈርድ ፡ ይመጣልና ።
በረሃና ፡ በእርሷም ፡ ያሉ ፡ ሁሉ ፡ ሐሤትን ፡ ያድርጉ ፡ ፲፪
የዱር ፡ ዛፎች ፡ ሁሉ ፡ በዚያን ፡ ጊዜ ፡
በእግዚአብሔር ፡ፊት ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
ይመጣልና፡አወን ፡ በምድር፡ ላይ፡ ሊፈርድ፡ ይመጣል ፡ ፲፫
እርሱም ፡ ዓለምን ፡ በጽድቅ ፡
ለአሕዛብም ፡ በቅንነት ፡ ይፈርዳል ።

መዝሙር ፡ ፺፮ ።

ስለ ትሩፋን ።

እግዚአብሔር ፡ነገሠ ፡ ምድር ፡ ሐሤትን ፡ ታድርግ ፡ ፩
ብዙ ፡ ደሴቶችም ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ።
ደመና ፡ ጭጋግም ፡ በዙሪያው ፡ ናቸው ፡ ፪
ጽድቅና ፡ ፍርድ ፡ የዙፋኑ ፡ መሠረት ፡ ናቸው ።
እሳት ፡ በፊቱ ፡ ይሄዳል ፡ ፫
ጠላቶቹንም ፡ በዙሪያው ፡ ያቃጥላል ።
መብረቆቹ ፡ ለዓለም ፡ አበሩ ፡ ፬
ምድር ፡ አየችና ፡ ተናወጠች ።

፭ ወአድባርኒ ፡ ተመስዉ ፡ ከመ ፡ ሠምዕ ።
እምቅድመ ፡ ገጹ ፡ ለእግዚአብሔር ።
እምቅድመ ፡ ገጹ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ኵላ ፡ ምድር ።
፮ ይነግራ ፡ ሰማያት ፡ ጽድቀ ፡ ዚአሁ ።
ወኵሎሙ ፡ አሕዛብ ፡ ርእዩ ፡ ስብሐቲሁ ።
፯ ይትኃፈሩ ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይሰግዱ ፡ ለግልፎ ።
ወእለ ፡ ይትሜክሑ ፡ በአማልክቲሆሙ ።
ወይሰግዱ ፡ሎቱ ፡ ኵሎሙ ፡ መላእክቲሁ ።
ሰምዐት ፡ ወተፈሥሐት ፡ ጽዮን ።
ወተሐሥያ ፡ አዋልደ ፡ ይሁዳ ።
፰ በእንተ ፡ ፍትሕከ ፡ እግዚኦ ።
፱ እስመ ፡ አንተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ባሕቲትከ ፡ ልዑል ፡
ዲበ ፡ ኵሉ ፡ ምድር ።
ፈድፋደ ፡ ተለዐልከ ፡ እምኵሉ ፡ አማልክት ።
፲ እለ ፡ታፈቅርዎ ፡ለእግዚአብሔር ፡ ጽልእዋ ፡ ለእኪት
የዐቅብ ፡እግዚአብሔር ፡ ነፍሰ ፡ ጻድቃኑ ።
ወያድኅኖሙ ፡ እምእደ ፡ ኃጥአን ።
፲፩ ብርሃ ፡ ሠረቀ ፡ ለጻድቃን ፡
ወለርቱዓነ ፡ ልብ ፡ ትፍሥሕት ።
፲፪ ይትፌሥሑ ፡ ጻድቃን ፡ በእግዚአብሔር ።
ወይገንዩ ፡ ለዝክረ ፡ ቅድሳቱ ።

መዝሙር ፡ ፺፯ ።

በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ ሰብሕዎ ለእግዚአብሔር ፡ ስብሐተ ፡ ሐዲሰ ።
እስመ ፡ መንክረ ፡ ግብረ ፡እግዚአብሔር ።
ወአድኀኖተ ፡ የማኑ ።
ወመዝራዕቱኒ ፡ ቅዱስ ።
፪ አርአየ ፡ እግዚአብሔር ፡ አድኅኖቶ ።
ወበቅድመ ፡ አሕዛብ ፡ ከሠተ ፡ ኪዳኖ ።
፫ ወተዘከረ ፡ ሣህሎ ፡ ለያዕቆብ ።
ወጽድቆኒ ፡ ለቤተ ፡ እስራኤል ።
ርእዩ ፡ ኵልክሙ ፡ አጽናፈ ፡ ምድር ። አድኅኖቶ ፡ ለአ
ምላክነ ።
፬ የብቡ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በኵሉ ፡ ምድር ።
ሰብሑ ፡ ወተፈሥሑ ፡ ወዘምሩ ።
፭ ዘምሩ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በመሰንቆ ።
በመሰንቆ ፡ ወበቃለ ፡ መዝሙር ።
፮ በቀርነ ፡ ዝብጦ ፡ ወበቃለ ፡ ቀርን ።
ወየብቡ ፡ በቅድመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ንጉሥ ።
፯ ወትትከወስ ፡ ባሕር ፡ በምልዓ ።
ዓለምኒ ፡ ወኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይነብሩ ፡ ውስቴታ ።
፰ ወአፍላግኒ ፡ ይጠፍሑ ፡ እደ ፡ ኅቡረ ።
አድባርኒ ፡ ይትሐሠዩ ።
፱ እስመ ፡ በሀየ ፡ ይኬንና ፡ ለምድር ።
ወይኬንና ፡ ለዓለም ፡ በጽድቅ ።
ወለአሕዛብኒ ፡ በርትዕ ።

መዝሙር ፡ ፺፰ ።

በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ እግዚአብሔር ፡ ነግሠ ፡ ደንገጹ ፡ አሕዛብ ።
ዘይነብር ፡ ዲበ ፡ ኪሩቤል ፡ አድለቅለቃ ፡ ለምድር ።
፪ እግዚአብሔር ፡ ዐቢይ ፡ በጽዮን ።
ወልዑል ፡ ውእቱ ፡ ላዕለ ፡ ኵሉ ፡ አሕዛብ ።
ኵሉ ፡ ይገኒ ፡ ለስምከ ፡ ዐቢይ ።
፫ እስመ ፡ ግሩም ፡ ወቅዱስ ፡ ውእቱ ።
፬ ክቡር ፡ ንጉሥ ፡ ፍትሐ ፡ ያፈቅር ።
፭ አንተ ፡ አጽናዕከ ፡ ለጽድቅ ፡ በኀይልከ ።
ፍትሐ ፡ ወጽድቀ ፡ ለያዕቆብ ፡ አንተ ፡ ገበርከ ።



ተራሮችም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ የተነማ ፡ ፭
ከምድር ፡ ሁሉ ፡ ጌታ ፡ ፊት ፡ የተነሳ ፡ እንደሰም ፡ ቀለጡ ።
ሰማያት ፡ የእርሱን ፡ ጽድቅ ፡ ነገሩ ፡ ፮
አሕዛብም ፡ ሁሉ ፡ ክብሩን ፡ አዩ ።
ለጣዖት ፡ የሚሰግዱ ፡ ሁሉ ፡ ፯
በጣዖቶቻቸውም ፡ የሚመኩ ፡ ይፈሩ ፡
መላእክቱ ፡ ሁሉ ፡ ሰገዱለት ።
አቤቱ ፡ ስለ ፡ ፍርድህ ፡ ፰
ጽዮን ፡ ሰምታ ፡ ደስ ፡ አላት ።
የይሁዳም ፡ ልጆች ፡ ደስ ፡ አላቸው ።
አንተ፡እግዚአብሔር በምድር፡ላይ፡ሁሉ፡ ልዑል፡ ነህና፡ ፱
በአማልክትም፡ ሁሉ፡ላይ፡ እጅግ ፡ ከፍ፡ከፍ ፡ ብለሃልና ።
እግዚአብሔርን ፡ የምትወዱ ፡ ክፉትን ፡ ጥሉ ፡ ፲
እግዚአብሔር ፡ የቅዱሳኑን ፡ ነፍሶች ፡ ይጠብቃል ።
ከኃጥአንም ፡ እጅ ፡ ያድናቸዋል ።
ብርሃን ፡ ለጻድቃን ፡ ፲፩
ደስታም ፡ ለልበ ፡ ቅኖች ፡ ወጣ ።
ጻድቃን ፡በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፡ ፲፪
ለቅድስናውም ፡ መታሰቢያ ፡ አመስግኑ ።

መዝሙር ፡ ፺፰ ።

ስለ ትሩፋን ።

እግዚአብሔርን ፡ በአዲስ ፡ ምስጋና ፡ አመስግኑ ፡ ፩
እግዚአብሔር ፡ ተአምራትን ፡ አድርጓልና ።
ቀኙ፡ የተቀደሰውም፡ ክንዱ ፡ ለእርሱ፡ ማዳንን፡አደረገ ።
እግዚአብሔር ፡ ማዳኑን ፡ አስታወቀ ፡ ፪
በአሕዛብም ፡ ፊት ፡ ጽድቁን ፡ ገለጠ ።
ለያዕቆብ ፡ ምሕረቱን ፡ ፫
ለእስራኤልም ፡ ቤት ፡ እውነቱን ፡ አሰበ ።
የምድር ፡ ዳርቻዎች ፡ ሁሉ፡የአምላካችንን ፡ማዳን፡አዩ ።
ምድር ፡ ሁሉ ፡ ሆይ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እልል ፡ በሉ ፡ ፬
አመስግኑ ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፡ ዘምሩም ።
ለእግዚአብሔር ፡ በመሰንቆ ፡ ፭
በመሰንቆና ፡ በዝማሬ ፡ ድምፅ ፡ ዘምሩ ።
በዋሽንትና ፡ በመለከት ፡ ድምፅ ፡ ፮
በንጉሥ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እልል ፡ በሉ ።
ባሕር ፡ በመላዋ ፡ ፯
ዓለምም ፡ በእርሷም ፡ የሚኖሩ ፡ ይናወጡ ።
ወንዞችም ፡ በአንድነት ፡ በእጅ ፡ ያጨብጭቡ ፡ ፰
ተራሮች ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ።
በምድር ፡ ሊፈርድ ፡ ይመጣልና ፡ ፱
ለዓለምም ፡ በጽድቅ ።
ለአሕዛብም ፡ በቅንነት ፡ ይፈርዳል ።

መዝሙር ፡ ፺፱ ።

ስለ ትሩፋን ።

እግዚአብሔር ፡ነገሠ ፡ አሕዛብ ፡ ይደንግጡ ፡ ፩
በኪሩቤል ፡ ላይ ፡ ተቀመጠ ፡ ምድር ፡ ትናወጥ ።
እግዚአብሔር ፡ በጽዮን ፡ ታላቅ ፡ ነው ፡
እርሱም ፡ በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለ ።
ግሩምና ፡ ቅዱስ ፡ ነውና ፡ ፫
ሁሉ ፡ ታላቅ ፡ ስምህን ፡ ያመሰግናሉ ።
የንጉሥ ፡ ክብር ፡ ፍርድን ፡ ይወዳል ፡ ፬
አንተ ፡ ቅንነትን ፡ አጸናህ ።
ለያዕቆብ ፡ ፍርድንና ፡ ጽድቅን ፡ አንተ ፡ አደረግህ ።

፭ ተለዐሉ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፈጣሪነ ።
ወይሰግዱ ፡ ሎቱ ፡ ታሕተ ፡ መከየደ ፡ እገሪሁ ።
፮ እስመ፡ ቅዱሳን፡ እሙንቱ፡ ሙሴ፡ወአሮን፡ በክህነቶሙ
ወሳሙኤልኒ ፡ ምስለ ፡ እለ ፡ ይጼውዑ ፡ ስሞ ።
ይጼውዕዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ውእቱኒ ፡ ይሰጠዎሙ
፯ ወይትናገሮሙ ፡ በዐምደ ፡ ደመና ።
ወየዐቅቡ ፡ ስምዖ ፤ ወትእዛዞ ፡ ዘወሀቦሙ ።
፰ እግዚኦ ፡ አምላክነ ፡ አንተ ፡ ሰማዕኮሙ ።
እግዚኦ ፡ አንተ ፡ ተሣሀልኮሙ ።
ወትትቤቀል ፡ በኵሉ ፡ ምግባሮሙ ።
፱ ተለዐሉ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክነ ።
ወይሰግዱ ፡ ሎቱ ፡ ውስተ ፡ ደብረ ፡ መቅደሱ ።
እስመ ፡ ቅዱስ ፡ ውእቱ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክነ ።

መዝሙር ፡ ፺፱ ።
በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ የብቡ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በኵሉ ፡ ምድር ።
፪ ተቀነዩ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በትፍሥሕት ።
ወባኡ ፡ ቅድሜሁ ፡ በሐሤት ።
፫ አእምሩ ፡ ከመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ውእቱ ፡ አምላክነ ።
ወውእቱ ፡ ፈጠረነ ፤ ወአኮ ፡ ንሕነ ።
ንሕነሰ ፡ ሕዝቡ ፡ ወአባግዐ ፡ መርዔቱ ።
፬ ባኡ ፡ ውስተ ፡ አናቅጺሁ ፡ በተጋንዮ ።
ወውስተ ፡ አዕጻዲሁ ፡ በስብሐት ፡ እመንዎ ።
፭ ወሰብሑ ፡ ለስሙ ፤ እስመ ፡ ኄር ፡ እግዚአብሔር ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
ወለትውልደ ፡ ትውልድ ፡ ጽድቁ ።

መዝሙ ፡ ፻ ።
በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ ምሕረተ ፡ ወፍትሐ ፡ አሐሊ ፡ ለከ ።
፪ እዜምር ፡ ወእሌቡ ፡ ፍኖተ ፡ ንጹሐ ።
ማእዜ ፡ ትመጽእ ፡ ኀቤየ ።
ወአሐውር ፡ በየዋሀተ ፡ ልብየ ፡ ማዕከለ ፡ ቤትየ ።
፫ ወኢረሰይኩ ፡ ቅድመ ፡ አዕይንትየ ፡ ግብረ ፡ እኩየ ።
ጸላእኩ ፡ ገበርተ ፡ ዐመፃ ።
፬ ወኢተለወኒ ፡ ልብ ፡ ጠዋይ ።
ሶበ ፡ ተግሕሠ ፡ እኩይ ፡ እምኔየ ፡ ኢያእመርኩ ።
፭ ዘየሐሚ ፡ ቢጾ ፡ በጽሚት ፡ ኪያሁ ፡ ሰደድኩ ።
ዕቡየ ፡ ዓይን ፡ ወስሡዐ ፡ ልብ ፡ ኢይትሐወል ፡ ምስሌየ
አዕይንትየሰ ፡ ኀበ ፡ መሃይምናነ ፡ ምድር ።
፮ ከመ ፡ አንብሮሙ ፡ ምስሌየ ።
ዘየሐውር ፡ በፍኖት ፡ ንጹሕ ፡ ውእቱ ፡ ይትለአከኒ ።
፯ ወኢይነብር ፡ ማእከለ ፡ ቤትየ ፡ ዘይገብር ፡ ትዕቢተ ።
ወኢየረትዕ ፡ ቅድሜየ ፡ ዘይነብብ ፡ ዐመፃ ።
በጽባሕ ፡ እቀትሎሙ ፡ ለኵሎሙ ፡ ኃጥአነ ፡ ምድር ።
፰ ከመ ፡ እሥርዎሙ ፡ እምሀገረ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለኵሎሙ ፡ ገበርተ ፡ ዐመፃ ።

መዝሙር ፡ ፻፩ ።
ጸሎተ ፡ ባሕታዊ ፡ ሶበ ፡ ይቴክዝ ፡ ወይክዑ ፡ ቅድመ ፡ እግዚአብሔር ስእለቶ ።

፩ ስምዐኒ ፡ እግዚኦ ፡ ጸሎትየ ።
ወይብጻሕ ፡ ቅድሜከ ፡ ገዓርየ ።
፪ ወኢትሚጥ ፡ ገጸከ ፡ እምኔየ ።
በዕለተ ፡ ምዳቤየ ፡ አጽምዕ ፡ እዘነከ ፡ ኀቤየ ።
አመ ፡ ዕለተ ፡ እጼውዐከ ፡ ፍጡነ ፡ ስምዐኒ ።



አምላካችንን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አድርጉት ፡ ፭
ቅዱስ ፡ ነውና ፡ ወደ ፡ እግሩ ፡ መረገጫ ፡ ስገዱ ።
ሙሴና ፡ አሮን ፡ በካህናቱ ፡ ዘንድ ፡ ፮
ሳሙኤልም ፡ ስሙን ፡ በሚጠሩ ፡ ዘንድ ፡ ናቸው ።
እግዚአብሔርን ፡ ጠሩት ፡ እርሱም ፡ መለሰላቸው ።
በደመና ፡ ዓምድም ፡ ተናገራቸው ፡ ፯
ምስክሩንና ፡ የሰጣቸውን ፡ ትእዛዝ ፡ ጠበቁ ።
አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ ሰማሃቸው ፡ ፰
አቤቱ ፡ አንተ ፡ ማርሃቸው ።
ሥራቸውን ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ ተበቀልሃቸው ።
አምላካችንን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አድርጉት ፡ ፱
አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡ ቅዱስ ፡ ነውና ።
በተቀደሰው ፡ ተራራውም ፡ ስገዱለት ።

መዝሙር ፡ ፺፱ ።
ስለ ትሩፋን ።

ምድር ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እልል ፡ በሉ ። ፩
በደስታም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ተገዙ ፡ ፪
በሐሴትም ፡ ወደ ፡ ፊቱ ፡ ግቡ ።
እግዚአብሔር ፡ እርሱ ፡ አምላክ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ዕወቁ ፡ ፫
እርሱ ፡ ሠራን ፡ እንጂ ፡ እኛ ፡ አይደለንም ፡
እኛስ ፡ ሕዝቡ ፡ የመሰማርያውም ፡ በጎች ፡ ነን ።
በመገዛት ፡ ወደ ፡ ደጆቹ ፡ ፬
በምስጋናም ፡ ወደ ፡ ግቢዎቹ ፡ ግቡ ፤
አመስግኑት ፡ ስሙንም ፡ ባርኩ ።
እግዚአብሔር ፡ ቸር ፡ ምሕረቱም ፡ ለዘላለም ፡ ፭
ጽድቁም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ነውና ።

መዝሙር ፡ ፻ ።
ስለ ትሩፋን ።

አቤቱ ፡ ምሕረትንና ፡ ፍርድን ፡ እቀኝልሃለሁ ፡ ፩
እዘምራለሁ ፡ ንጹሕ ፡ መንገድንም ፡ አስተውላለሁ ። ፪
ወደ ፡ እኔ ፡ መቼ ፡ ትመጣለህ ?
በቤቴ ፡ መካከል ፡ በልቤ ፡ ቅንነት ፡ እሄዳለሁ ።
በዓይኔ ፡ ፊት ፡ ክፉን ፡ ነገር ፡ አላኖርሁም ። ፫
ሕግ ፡ ተላላፊዎችን ፡ ጠላሁ ።
ጠማማ ፡ ልብም ፡ አልተጠጋኝም ፡ ፬
ክፉ ፡ ከእኔ ፡ በራቀ ፡ ጊዜ ፡ አላወቅሁም ።
ባልንጀራውን፡በቀስታ፡የሚያማን፡እርሱን፡አሳደድሁ ፡ ፭
በዓይኑ ፡ ትዕቢተኛ ፡ የሆነውና ፡ ልቡም ፡ የሚሳሳው ፡
ከእኔ ፡ ጋራ ፡ አይተባበርም ።
ከእኔ ፡ ጋራ ፡ ይኖሩ ፡ ዘንድ ፡ ፮
ዓይኖቼ ፡ በምድር ፡ ምእመናን ፡ ላይ ፡ ናቸው ፤
በቀና ፡ መንገድ ፡ የሚሔድ ፡ እርሱ ፡ ያገለግለኛል ።
ትዕቢትን የሚያደርግ በቤቴ መካከል አይኖርም ። ፯
ዓመፅን ፡ የሚናገር ፡ በዓይኔ ፡ ፊት ፡ አይቀናም ።
ዓመፃ ፡ የሚያደርጉትን ፡ ሁሉ ፡ ከእግዚአብሔር ፡
አገር ፡ አጠፋቸው ፡ ዘንድ ፡
የምድርን ፡ ኃጢአተኞች ፡ ሁሉ ፡ በማለዳ ፡ አገድላቸዋለሁ ።

መዝሙር ፡ ፻፩ ።
እያዘነ ፡ ልመናውንና ፡ ጸሎቱን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፊት ፡ ባቀረበ ፡ ጊዜ ።

አቤቱ ፡ ጸሎቴን ፡ ስማኝ ፡ ፩
ጩኸቴም ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ይድረስ ።
በመከራዬ ፡ ቀን ፡ ፊትህን ፡ ከኔ ፡ አትመልስ ፡ ፪
ጆሮህን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አዘንብል ።

፫ እስመ ፡ ኀልቀ ፡ ከመ ፡ ጢስ ፡ መዋዕልየ ።
ወነቅጸ ፡ ከመ ፡ ሣዕር ፡ አዕፅምትየ ።
ተቀሠፍኩ ፡ ወየብሰ ፡ ከመ ፡ ሣዕር ፡ ልብየ ።
፬ እስመ ፡ ተረስዐኒ ፡ በሊዐ ፡ እክል ።
፭ እምቃለ ፡ ገዓርየ ፡ ጠግዐ ፡ ሥጋየ ፡ ዲበ ፡ አዕፅምትየ።
፮ ወኮንኩ ፡ ከመ ፡ አድግ ፡ መረብ ፡ ዘገዳም ።
ወኮንኩ ፡ ከመ ፡ ጉጓ ፡ ውስተ ፡ ቤት ፡ ሌሊት ።
፯ ተጋህኩ ፡ ወኮንኩ፡ከመ፡የፍ፡ባሕታዊ፡ውስተ፡ናሕስ።
፰ ወዘለፉ ፡ አሜረ ፡ ይጼዕሉኒ ፡ ጸላእትየ ።
ወእለኒ ፡ ይሰዱኒ ፡ ይሰከተዩ ፡ ላዕሌየ ።
፱ እስመ ፡ ሐመደ ፡ ከመ ፡ እክል ፡ ቀማሕኩ ።
ወስቴየኒ ፡ ምስለ ፡ አንብዕየ ፡ ሰተይኩ ።
እምገጸ ፡ መቅሠፍተ ፡ መዓትከ ።
፲ እስመ ፡ አንሣእከኒ ፡ ወነፃሕከኒ ።
፲፩ ወመዋዕልየኒ ፡ ከመ ፡ ጽላሎት ፡ ኀለፈ ።
ወአነሂ ፡ ከመ ፡ ሣእር ፡ የበስኩ ።
፲፪ አንተሰ ፡ እግዚኦ ፡ ለዓለም ፡ ትነብር ።
ወዝክርከኒ ፡ ለትውልደ ፡ ትውልድ ።
፲፫ ተንሥእ ፡ እግዚኦ ፡ ወተሣሃላ ፡ ለጽዮን ።
እስመ ፡ ጊዜሃ ፡ ውእቱ ፡ ከመ ፡ ትሣሃላ ፡ ወበጽሐ ፡ ዕድሜሃ ።
፲፬ እስመ ፡ ሠምሩ ፡ አግብርቲከ ፡ እበኒሃ ።
ወአክበርዋ ፡ ለመሬታ ።
፲፭ ወይፈርሁ ፡ አሕዛብ ፡ ስመከ ፡ እግዚኦ ።
ወዙሎሙ ፡ ነገሥት ፡ ለስብሐቲከ ።
፲፮ እስመ ፡ የሐንጻ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለጽዮን ።
ወያስተርኢ ፡ በስብሐቲሁ ።
፲፯ ወነጸረ ፡ ላዕለ ፡ ጸሎተ ፡ ነዳይ ።
ወኢተቈጥዓ ፡ ሥዕለቶሙ ።

፲፰ ወተጽሕፈት ፡ ዛቲ ፡ ለካልእ ፡ ትውልድ ።
ሕዝብ ፡ ዘይትፈጠር ፡ ይሴብሖ ፡ ለእግዚአብሔር ።
እስመ ፡ ሐወጸ ፡ እምሰማይ ፡ መቅደሱ ።
፲፱ እግዚአብሔር ሐወጸ ፡ እምሰማይ ፡ ዲበ ፡ ምድር ።
፳ ከመ ፡ ይስማዕ ፡ ገዓሮሙ ፡ ለሙቁሓን ።
ወከመ ፡ ያሕይዎሙ ፡ ለደቂቀ ፡ ቅቱላን ።
፳፩ ከመ ፡ ይንግሩ ፡ በጽዮን ፡ ስመ ፡ እግዚአብሔር ።
ወስብሐቲሁኒ ፡ በኢየሩሳሌም ።
፳፪ ሶበ ፡ ተጋብኡ ፡ አሕዛብ ፡ ሕቡረ ።
ወነገሥትኒ ፡ ከመ ፡ ይትቀነዩ ፡ ለእግዚአብሔር ።
፳፫ ወተሰጥዎሙ ፡ በፍኖተ ፡ ኃይሉ ።
፳፬ ንግረኒ ፡ ውኅዶን ፡ ለመዋዕልየ ። ወኢትሰደኒ ፡ በመ
ንፈቀ ፡ ዓመትየ ።
ለትውልደ ፡ ትውልድ ፡ ዓመቲከ ።
፳፭ አንተ ፡ እግዚኦ ፡ አቅደምከ ፡ ሣርሮታ ፡ ለምድር ።
ወግብረ ፡ እደዊከ ፡ እማንቱ ፡ ሰማያት ።
፳፮ እማንቱሰ ፡ ይትሀጐላ ፡ ወአንተሰ ፡ ትሄሉ ።
ወዙሉ ፡ ከመ ፡ ልብስ ፡ ይበሊ ።
ወከመ ፡ ሞጣሕት ፡ ትዌልጦሙ ፡ ወይትዌለጡ ።
፳፯ አንተሰ ፡ አንተ ፡ ከመ ። ወዓመቲከኒ ፡ ዘኢየኀልቅ ።
፳፰ ደቂቀ ፡ አግብርቲከ ፡ ይነብርዋ ።
ወዘርዖሙኒ ፡ ለዓለም ፡ ይጸንዕ ።

መዝሙር ፡ ፻፪ ።

በእንተ ትሩፋን ።

፩ ትባርኮ ፡ ነፍስየ ፡ ለእግዚአብሔር ።
ወዙሉ ፡ አዕፅምትየ ፡ ለስሙ ፡ ቅዱስ ።
፪ ትባርኮ ፡ ነፍስየ ፡ ለእግዚአብሔር ።
፫ ወኢትርሳእ ፡ ዘሎ ፡ ስብሐቲሁ ።



ዘመኔ ፡ እንደ ፡ ጢስ ፡ ተኖ ፡ አልቃለችና ፡ ፫
አጥንቶቼም ፡ እንደ ፡ መቃጠያ ፡ ተቃጥለዋልና ፡
በጠራሁህ ፡ ቀን ፡ ፈጥነህ ፡ ስማኝ ።
እህል ፡ መብላት ፡ ተረስቶኛልና ፡ ፬
ተቀሠፍሁ ፡ ልቤም ፡ እንደ ፡ ሣር ፡ ደረቀ ።
ከጩኸቴ፡ድምፅ የተነሣ አጥንቶቼ ከሥጋዬ ጋራ ፡ ተጣበቁ ። ፭
እንደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ እርኩም ፡ መሰልሁ ፡ ፮
በፈረሰ ፡ ቤት ፡ እንዳለ ፡ እንደ ፡ ጉጉት ፡ ሆንሁ ።
ተጋሁ ፡ በሰገነትም ፡ እንደሚኖር ፡ ብቸኛ ፡ ድንቢጥ ፡ ሆንሁ ። ፯
ጠላቶቼ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ ይሰድቡኛል ፡ ፰
የሚያሳድዱኝም ፡ ተማማሉብኝ ።
አንሥተኸኛልና ፡ ጥለኸኝማልና ፡ ፱
ከቍጣህና ፡ ከመዓትህ ፡ የተነሣ ።
አመድን ፡ እንደ ፡ እህል ፡ ቃምሁት ፡ ፲
መጠጤንም ፡ ከዕንባዬ ፡ ጋራ ፡ ቀላቀልሁት ።
ዘመኖቼ ፡ እንደ ፡ ጥላ ፡ አዘንብለዋል ፡ ፲፩
እኔም ፡ እንደ ፡ ሣር ፡ ደርቄአለሁ ።
አንተ ፡ ግን ፡ አቤቱ ፡ ለዘላለም ፡ ትኖራለህ ፡ ፲፪
መታሰቢያህም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ነው ።
አንተ ፡ ተነሣ ፡ ጽዮንንም ፡ ይቅር ፡ በላት ፡ ፲፫
የምሕረቷ ፡ ጊዜ ፡ ነውና ፡ ዘመኗም ፡ ደርሷልና ።
ባሮችህም ፡ ደንጊያዎቿን ፡ ወደዋልና ፡ ፲፬
ለመሬቷም ፡ አዝነዋልና ።
አቤቱ ፡ አሕዛብ ፡ ስምህን ፡ ፲፭
ነገሥታትም ፡ ሁሉ ፡ ክብርህን ፡ ይፈራሉ ።
እግዚአብሔር ፡ ጽዮንን ፡ ይሠራታልና ፡ ፲፮
በክብሩም ፡ ይገለጣልና ።
ወደ ፡ ችጋረኞች ፡ ጸሎት ፡ ተመለከተ ፡ ፲፯
ልመናቸውንም ፡ አልናቀም ።

ይህ ፡ ለሚመጣው ፡ ትውልድ ፡ ይጻፍ ፡ ፲፰
የሚፈጠርም ሕዝብ ለእግዚአብሔር እልል ይላል ፡
እግዚአብሔር ፡ ከመቅደሱ ፡ ከፍታ ፡ ሆኖ ፡ ተመልክቷልና ፡ ፲፱
ከሰማይ ፡ ሆኖ ፡ ምድርን ፡ አይቷልና ።
የታሰሩትን ፡ ጩኸት ፡ ይሰማ ፡ ዘንድ ፡ ፳
የተገደሉትን ፡ ልጆች ፡ ያድን ፡ ዘንድ ።
የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ በጽዮን ፡ ፳፩
ምስጋናውንም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ይናገሩ ፡ ዘንድ ፡
አሕዛብም ፡ በአንድነት ፡ በተሰበሰቡ ፡ ጊዜ ፡ ፳፪
መንግሥታት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ይገዙ ፡ ዘንድ ።
በኃይሉ ፡ ጐዳና ፡ መለሰለት ፡ ፳፫
የዘመኔን ፡ እነስተኛነት ፡ ንገረኝ ።
በዘመኔ ፡ እኩሌታ ፡ አትውሰደኝ ፡ ፳፬
ዓመቶችህ ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ናቸው ።
አቤቱ ፡ አንተ ፡ ከጥንት ፡ ምድርን ፡ መሠረትህ ፡ ፳፭
ሰማያትም ፡ የእጅህ ፡ ሥራ ፡ ናቸው ።
እነርሱ ፡ ይጠፋሉ ፡ አንተ ፡ ግን ፡ ትኖራለህ ፡ ፳፮
ሁላቸው ፡ እንደ ፡ ልብስ ፡ ያረጃሉ ።
እንደ ፡ መጐናጸፊያም ፡ ትለውጣቸዋለህ ፡ ይለወጣሉ ።
አንተ ፡ ግን ፡ ያው ፡ አንተ ፡ ነህ ፡ ፳፯
ዓመቶችህም ፡ ከቶ ፡ አያልቁም ።
የባሮችህም ፡ ልጆች ፡ ይኖራሉ ፡ ፳፰
ዘራቸውም ፡ ለዘላለም ፡ ትጸናለች ።

መዝሙር ፡ ፻፪ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

ነፍሴ ፡ ሆይ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ባርኪ ፡ ፩
አጥንቶቼ ፡ ሁሉ ፡ ለተቀደሰ ፡ ስሙ ።
ነፍሴ ፡ ሆይ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ባርኪ ፡ ፪
ምስጋናውንም ፡ ሁሉ ፡ አትርሺ ። ፫

፫ ዘይሥሬ ለከ ኵሎ ኀጢአተከ ። ዘይፌውሰከ እምኵሉ ደዌከ ።
፬ ዘያድኅና ፡ እሙስና ፡ ለሕይወትከ ።
ዘይኬልለከ ፡ በሣህሉ ፡ ወበምሕረቱ ።
፭ ዘያጸግበ ፡ እምበረከቱ ፡ ለፍትወትከ ።
ዘይሔድሳ ፡ ከመ ፡ ንስር ፡ ለውርዙትከ ።
፮ ገባሬ ፡ ሣህል ፡ እግዚአብሔር ።
ወይሬትዕ ፡ ለኵሉ ፡ ግፉዓን ።
፯ አርአየ ፍናዊሁ ለሙሴ ። ወለደቂቀ እስራኤል ሥምረቶ ።
፰ መሐሪ ፡ ወመስተሣህል ፡ እግዚአብሔር ።
ርኁቀ ፡ መዓት ፡ ወብዙኅ ፡ ምሕረት ፡ ወጻድቅ ።
፱ ኢይቀሥፍ ፡ ወትረ ፤ ወኢይትመዐዕ ፡ ዘልፈ ።
፲ አኮ ፡ በከመ ፡ ኀጢአትነ ፡ ዘገብረ ፡ ለነ ።
ወኢፈደየነ ፡ በከመ ፡ አበሳነ ።
፲፩ ወበከመ ፡ ልዑል ፡ ሰማይ ፡ እምድር ።
አጽንዐ ምሕረቶ እግዚአብሔር ላዕለ እለ ይፈርህዎ ።
፲፪ ወበከመ ፡ ይርኅቅ ፡ ሠርቅ ፡ እምዐረብ ።
አርኀቀ ፡ እምኔነ ፡ ኀጢአተነ ።
፲፫ ወበከመ ፡ ይምሕር ፡ አብ ፡ ውሉዶ ።
ከማሁ፡ ይምሕሮሙ፡ እግዚአብሔር ለእለ፡ይፈርህዎ ፤
፲፬ እስመ ፡ ውእቱ ፡ የአምር ፡ ፍጥረተነ ።
ተዘከር ፡ እግዚኦ ፡ ከመ ፡ መሬት ፡ ንሕነ ።
፲፭ ወሰብእሰ ፡ ከመ ፡ ሣዕር ፡ መዋዕሊሁ ።
ወከመ ፡ ጽጌ ፡ ገዳም ፡ ከማሁ ፡ ይፈሪ ።
፲፮ እስመ፡መንፈስ፡ ይወፅእ፡ እምኔሁ ፡ ወኢይሄሉ፡ እንከ ።
ወኢየአምር ፡ እንከ ፡ መካኖ ።
፲፯ ሣህሉሰ፡ለእግዚአብሔር እምዓለም፡ወእስከ፡ለዓለም ።
ዲበ ፡ እለ ፡ ይፈርህዎ ።
ወጽድቁኒ ፡ ዲበ ፡ ትውልደ ፡ ትውልድ ።
፲፰ ለእለ፡የዐቅቡ፡ሕጎ። ወይዜከሩ፡ትእዛዞ፡ ከመ፡ይግበሩ ።
፲፱ እግዚአብሔር ፡ አስተዳለወ ፡ መንበሮ ፡ በሰማያት።
ወኵሎ ፡ ይኴንን ፡ በመንግሥቱ ።
ባርክዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ኵልክሙ ፡ መላእክቲሁ ።
፳ ጽኑዓን ፡ ወኀያላን ፡ እለ ፡ ትገብሩ ፡ ቃሎ ።
ወእለ ፡ ትሰምዑ ፡ ቃለ ፡ ነገሩ ።
፳፩ ይባርክዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ኵሉ ፡ ኀይሉ ።
ላእካኑ ፡ እለ ፡ ይገብሩ ፡ ፈቃዶ ።
ይባርክዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ኵሉ ፡ ተግባሩ ።
፳፪ ውስተ ፡ ኵሉ ፡ በሐውርት ፡ መለኮቱ ።
ትባርኮ ፡ ነፍስየ ፡ ለእግዚአብሔር ።

መዝሙር ፡ ፻፫ ።

በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ ትባርኮ ፡ ነፍስየ ፡ ለእግዚአብሔር ።
እግዚኦ ፡ አምላኪየ ፡ ጥቀ ፡ ዐበይከ ፡ ፈድፋደ ።
አሚነ ፡ ወዕበየ ፡ ስብሐት ፡ ለበስከ ።
፪ ወለበስከ ፡ ብርሃነ ፡ ከመ ፡ ልብስ ።
ወረበብኮ ፡ ለሰማይ ፡ ከመ ፡ ሠቅ ።
፫ ዘይጠፍር ፡ በማይ ፡ ጽርሖ ።
ወረሰየ ፡ ደመና ፡ መከየዶ ፡ ዘየሐውር ፡ በክንፈ ፡ ነፋስ።
፬ ዘይሬስዮሙ ፡ ለመላእክቲሁ ፡ መንፈሰ ።
ወለእለ ፡ ይትለአክዎ ፡ ነደ ፡ እሳት ።
ሣረራ ፡ ለምድር ፡ ወአጽንዓ ።
፭ ከመ ፡ ኢታንቀልቅል ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ።
፮ ወቀላይኒ ፡ ከመ ፡ ልብስ ፡ ዐጽፉ ።
ውስተ ፡ አድባር ፡ ይቀውሙ ፡ ማያት ።



ኃጢአትሽን ፡ ሁሉ ፡ ይቅር ፡ የሚል ፤ ፫
ደዌሽንም ፡ ሁሉ ፡ የሚፈውስ ።
ሕይወትሽን ፡ ከጥፋት ፡ የሚያድናት ፤ ፬
በምሕረቱና ፡ በቸርነቱ ፡ የሚጋርድሽ ።
ምኞትሽን ፡ ከበረከቱ ፡ የሚያጠግባት ፤ ፭
ጕልማስነትሽን ፡ እንደ ፡ ንስር ፡ ያድሳል ።
እግዚአብሔር ፡ ይቅርታ ፡ አድራጊ ፡ ነው ፤ ፮
ለተበደሉ ፡ ሁሉ ፡ ይፈርዳል ።
ለሙሴ ፡ መንገዱን ፡ አስታወቀ ፤ ፯
ለእስራኤል ፡ ልጆችም ፡ አደራረጉን ።
እግዚአብሔር ፡ መሐሪና ፡ ይቅር ፡ ባይ ፡ ነው ፤ ፰
ከቍጣ ፡ የራቀ ፡ ምሕረቱም ፡ የበዛ ፡ ነው ።
ሁል ፡ ጊዜም ፡ አይቀሥፍም ፡ ለዘላለምም፡አይቆጣም ፤ ፱
እንደ ፡ ኀጢአታችን ፡ አላደረገብንም ፤ ፲
እንደ ፡ በደላችንም ፡ አልከፈለንም ።
ሰማይ ፡ ከምድር ፡ ከፍ ፡ እንዲል ፤ ፲፩
እንዲሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ምሕረቱን ፡ በሚ
ፈሩት ፡ ላይ ፡ አጠነከረ ።
ምሥራቅ ፡ ከምዕራብ ፡ እንደሚርቅ ፤ ፲፪
ኃጢአታችንን ፡ ከእኛ ፡ አራቀ ።
አባት ፡ ለልጆቹ ፡ እንዲራራ ፤ ፲፫
እንዲሁ ፡ እግዚአብሔር ለሚፈሩት ፡ ይራራል ።
ፍጥረታችንን ፡ እርሱ ፡ ያውቃልና ፤ ፲፬
እኛም ፡ አፈር ፡ እንደ ፡ ሆንን ፡ አሰብ ።
ሰውስ ፡ ዘመኑ ፡ እንደ ፡ ሣር ፡ ነው ፤ ፲፭
እንደ ፡ ዱር ፡ አበባ ፡ እንዲሁ ፡ ያብባል ።
ነፋስ ፡ በነፈሰበት ፡ ጊዜ ፡ ያልፋልና ፤ ፲፮
ስፍራውንም ፡ ደግሞ ፡ አያውቀውም ።
የእግዚአብሔር ፡ምሕረት ግን ከዘላለም እስከ ዘላለም በሚፈሩት ላይ ፲፯
ጽድቁም ፡ በልጅ ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ ነው ።
ቃል ፡ ኪዳኑን ፡ ለሚጠብቁ ፤ ፲፰
ትእዛዙንም ፡ ያደርጓት ፡ ዘንድ፡ ለሚያስቡ ።
እግዚአብሔር ፡ ዙፋኑን ፡ በሰማይ ፡ አዘጋጀ ፤ ፲፱
መንግሥቱም ፡ ሁሉን ፡ ትገዛለች ።
ቃሉን ፡ የምታደርጉ ፡ ብርቱዎችና ፡ ኀይለኞች ፤ ፳
የቃሉንም ፡ድምፅ ፡ የምትሰሙ ፡ መላእክት ፡ ሁሉ ፤
እግዚአብሔርን ፡ ባርኩ ።
ሠራዊቱ ፡ ሁሉ ፤
ፈቃዱን ፡ የምታደርጉ ፤ ፳፩
አገልጋዮቹ ፤ እግዚአብሔርን ፡ ባርኩ ።
ፍጥረቶቹ ፡ ሁሉ ፡ በግዛቱ ፡ ስፍራ ፡ ሁሉ ፤ እግዚአ ፳፪
ብሔርን ፤ ባርኩ ፤
ነፍሴ ፡ ሆይ ፡ እግዚአብሔርን ባርኪ ።

መዝሙር ፡ ፻፫ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

ነፍሴ ፡ ሆይ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ባርኪ ፤ ፩
አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ እጅግ ፡ ታላቅ ፡ ነህ ፤
ክብርንና ፡ ግርማን ፡ ለበስህ ።
ብርሃንን ፡ እንደ ፡ መጐናጸፊያ ፡ የተጐናጸፍህ ፤ ፪
ሰማይንም ፡ እንደ ፡ መጋረጃ ፡ የዘረጋህ ።
እልፍኝህን ፡ በውኃ ፡ የሠራህ ፤ ፫
ሠረገላህን ፡ ደመና ፡ ያደረግህ ፤
በነፋስ ፡ ክንፍም ፡ የምትሄድ ።
መላእክቱን ፡ መንፈስ ፡ የሚያደርግ ፤ ፬
አገልጋዮቹንም ፡ የምትንበለበል ፡ እሳት ።
ለዘላለም ፡ እንዳትናወጥ ፤ ፭
ምድርን ፡ በመሠረቷ ፡ ላይ ፡ መሠረታት ።
በጥልቅ ፡ እንደ ፡ ልብስ ፡ ከደንሃት ፤ ፮
በተራሮችም ፡ ላይ ፡ ውኆች ፡ ይቆማሉ ።

፯ እምተግሣጽከ ፡ ይጕዩ ። ወእምድምፀ ፡ ነጐድጓድከ ፡
ይደነግፁ ።
፰ የዐርጉ ፡ አድባረ ፡ ወይወርዱ ፡ ገዳመ ።
ውስተ ፡ ብሔር ፡ ኀበ ፡ ሣረርኮሙ ፡ መሠረትኮሙ ።
፱ ወሠሬምኮሙ ፡ እምኀበ ፡ ኢየኀልፉ ።
ከመ ፡ ኢይትመየጡ ፡ ወኢይክድንዋ ፡ ለምድር ።
፲ ዘይፌኑ ፡ አንቅዕተ ፡ ውስተ ፡ ቈላት ።
ማዕከለ ፡ አድባር ፡ የኀልፉ ፡ ማያት ።
፲፩ ወያሰትዩ ፡ ለኵሉ ፡ አርዌ ፡ ገዳም ።
ወይትዌከፉ ፡ ሐለስትዮታት ፡ ለጽምዖሙ ።
፲፪ ወያጸልሉ ፡ ህየ ፡ አዕዋፈ ፡ ሰማይ ።
ወይነቅዉ ፡ በማእከለ ፡ ጸላዕት ።
፲፫ ዘይሠቅዮሙ ፡ ለአድባር ፡ እምውሳጥያቲሆሙ ።
እምፍሬ ፡ ተግባርከ ፡ ትጸግብ ፡ ምድር ።
ዘያበቊል ፡ ሣዕረ ፡ ለእንስሳ ።
ወሐመልማለ ፡ ለቅኔ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ።
፲፬ ከመ ፡ ያውፅእ ፡ እክለ ፡ እምድር ።
፲፭ ወይን ያስተፌሥሕ ልበ ሰብእ ። ወቅብዕ ለአብርሆ ገጽ ።
እክል ፡ ያፀንዕ ፡ ኀይለ ፡ ሰብእ ።
፲፮ ወይጸግቡ ኵሉ ዕፀወ ገዳም ። አርዘ ሊባኖስ ዘተከልከ ።
፲፯ ወበህየ ፡ ይትዋለዱ ፡ አዕዋፍ ።
ወይትጋወሮን ፡ ቤተ ፡ ሄሮድያዋስ ።
፲፰ አድባር ፡ ነዋኃት ፡ ለሀየላት ።
ወጸላዕት ፡ ምጕያዮን ፡ ለግሔ ።
፲፱ ወገበርከ ወርኀ በዕድሜሁ ። ፀሐይኒ አእመረ ምዕራቢሁ ።
፳ ታመጽእ ፡ ጽልመተ ፡ ወይከውን ፡ ሌሊተ ።
ወይወፅኡ ፡ ቦቱ ፡ ኵሉ ፡ አርዌ ፡ ገዳም ።
፳፩ ዕጓለ ፡ አናብስት ፡ ይጥሕሩ ፡ ወይመሥጡ ።
ወይስእሉ ፡ ኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡ሲሳዮሙ ።
፳፪ ወእምከመ ፡ ሠረቀ ፡ ፀሐይ ፡ የአትዉ ።
ወይውዕሉ ፡ ውስተ ፡ ግበቢሆሙ ።
፳፫ ይወፍር ፡ ሰብእ ፡ ውስተ ፡ ተግባሩ ።
ይውዕል ፡ ወይትቀነይ ፡ እስከ ፡ ይመሲ ።
፳፬ ጥቀ ዐቢይ ግብርከ እግዚኦ ። ወኵሉ በጥበብ ገበርከ ።
መልአ ፡ ምድረ ፡ ዘፈጠርከ ።
፳፭ ዛቲ ፡ ባሕር ፡ ዐባይ ፡ ወረሓብ ።
ህየ ፡ ዘይትሐወስ ፡ ዘአልቦ ፡ ኍልቍ ።
እንስሳ ፡ ዐበይት ፡ ምስለ ፡ ደቃቅ ።
፳፮ ህየ ፡ የሐውራ ፡ አሕማር ።
ከይሲ ፡ ዘፈጠርከ ፡ ይሣለቅ ፡ ላዕሌሆሙ ።
፳፯ ወኵሉ ፡ ይሴፎ ፡ በኀቤከ ። ተሀቦሙ ፡ ሲሳዮሙ ፡
በጊዜሁ ።
፳፰ ወእምከመ ፡ ወሀብኮሙ ፡ ያስተጋብኡ ።
ወፈቲሐከ ፡ እዴከ ፡ ታጸግብ ፡ ለኵሉ ፡ እምሕረትከ ።
፳፱ እመሰ ፡ ሜጥከ ፡ ገጸከ ፡ ይደነግፁ ።
ታወፅእ ፡ መንፈሶሙ ፡ ወየኀልቁ ።
ወይገብኡ ፡ ውስተ ፡ መሬቶሙ ።
፴ ትፌኑ ፡ መንፈሰከ ፡ ወይትፈጠሩ ።
ወትሔድስ ፡ ገጸ ፡ ለምድር ።
፴፩ ለይኩን ፡ ስብሐቲሁ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ለዓለም ።
ይትፌሣሕ ፡ እግዚአብሔር ፡ በተግባሩ ።
፴፪ ዘይኔጽራ ፡ ለምድር ፡ ወይሬስያ ፡ ከመ ፡ ትርዐድ ።
ዘይገሥሦሙ ፡ ለአድባር ፡ ወይጠይሱ ።



ከዘለፋህም ፡ ሸሹ ፡ ፯
ከነጐድጓድህም ፡ ድምፅ ፡ ኰበለሉ ።
ወደ ፡ ተራሮች ፡ ወጡ ፡ ፰
ወደ፡ቈላዎችና ፡ ወደ፡ አዘጋጀህላቸው ፡ ስፍራ፡ ወረዱ ።
እንዳያልፏትም ፡ ድንበርን ፡ አደረግህላቸው ፡ ፱
ምድርን ፡ ይከድኑ ፡ ዘንድ ፡ እንዳይመለሱ ።
ምንጮችን ፡ ወደ ፡ ቆላዎች ፡ ይልካል ፡ ፲
በተራሮች ፡ መካከል ፡ ውኆች ፡ ያልፋሉ ።
የዱር ፡ አራዊትን ፡ ሁሉ ፡ ያጠጣሉ ፡ ፲፩
የበረሃ ፡ አህዮችም ፡ ከጥማቸው ፡ ይረካሉ ።
የሰማይም ፡ወፎች ፡ በእነርሱ ፡ዘንድ ፡ያድራሉ ፡ ፲፪
በቅርንጫፎችም ፡ መካከል ፡ ይጮኻሉ ።
ተራሮችን ፡ ከላይ ፡ የሚያጠጣቸው ፡ ፲፫
ከሥራህ ፡ ፍሬ ፡ ምድር ፡ ትጠግባለች ።
እንጀራን ፡ ከምድር ፡ ያወጣ ፡ ዘንድ ፡ ፲፬
ለምለሙን ፡ ለሰው ፡ ልጆች ፡ ጥቅም ፡
ሣርንም ፡ ለእንስሳ ፡ ያበቅላል ።
ወይን ፡ የሰውን ፡ ልብ ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ፡ ፲፭
ዘይትም ፡ ፊትን ፡ ያበራል ፡
እህልም ፡ የሰውን ፡ ጉልበት ፡ ያጠነክራል ።
የእግዚአብሔር ፡ ዛፎች ፡ ፲፮
እርሱም፡የተከላቸው፡ የሊባኖስ ፡ ዝግባዎች፡ይጠግባሉ ።
በዚያም ፡ ወፎች ፡ ይዋለዳሉ ፡ ፲፯
የሽመላ ፡ ቤትም ፡ የእርሱ ፡ ጎረቤት ፡ ነው ።
ረጃጅም ፡ ተራራዎች ፡ ለዋልያዎች ፡ ፲፰
ድንጋዮችም ፡ ለእሽኮኮዎች ፡ መሸሸ ፡ ናቸው ።
ጨረቃን ፡ ለጊዜዎች ፡ አደረገ ፡ ፲፱
ፀሐይም ፡ መግቢያውን ፡ ያውቃል ።
ጨለማ ፡ ታደርጋለህ ፡ ሌሊትም ፡ ይሆናል ፡ ፳
በነርሱም ፡ የዱር ፡ አራዊት ፡ ሁሉ ፡ ይወጡበታል ።
የአንበሳ ፡ ግልገሎች ፡ ለመንጠቅ ፡ ይጮኻሉ ፡ ፳፩
ከእግዚአብሔር ፡ ምግባቸውን ፡ ይሻሉ ።
ፀሐይ ፡ ስትወጣ ፡ ይሰበሰባሉ ፡ ፳፪
በየዋሻቸውም ፡ ይተኛሉ ።
ሰው ፡ ወደ ተግባሩ ፡ ይሠማራል ፡ ፳፫
እስኪመሽም ፡ ድረስ ፡ ሥራውን ፡ ያከናውናል ።
አቤቱ ፡ ሥራህ ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ነው ፡ ፳፬
ሁሉን ፡ በጥበብ ፡ አደረግህ ።
ምድርም ፡ ከፍጥረትህ ፡ ተሞላች ።
ይህቺ ፡ ባሕር ፡ ታላቅና ፡ ሰፊ ፡ ናት ፡ ፳፭
በዚያ ፡ ስፍር ፡ ቍጥር ፡ የሌለው ፡ ተንቀሳቃሽ ፡
ታላላቆችና ፡ ታናናሾች ፡ እንስሶች ፡ አሉ ።
በዚያ ፡ ላይ ፡ መርከቦች ፡ ይሄዳሉ ፡ ፳፮
በዚያም ፡ ላይ፡የፈጠርኸው ፡ ዘንዶ ፡ ይጫወትበታል
ምግባቸውን ፡ በየጊዜው ፡ ትሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ ፳፯
እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ አንተን ፡ ተስፋ ፡ ያደርጋሉ ።
በሰጠሃቸውም ፡ ጊዜ ፡ ይሰበሰባሉ ፡ ፳፰
እጅህን፡ ትዘረጋለህ፤ ከመልካም፡ ነገርም፡ ይጠግባሉ ።
ፊትህን ፡ ስትሠውር ፡ ይደነግጣሉ ፡ ፳፱
ነፍሳቸውን ፡ ታወጣለህ ፡ ይሞታሉም ፡
ወደ ፡ መሬትነታቸውም ፡ ይመለሳሉ ።
መንፈስህን ፡ ትልካለህ ፡ ይፈጠራሉም ፡ ፴
የምድርንም ፡ ፊት ፡ ታድሳለህ ።
የእግዚአብሔር ፡ ክብር ፡ ለዘላለም ፡ ይሁን ፡ ፴፩
እግዚአብሔር ፡ በሥራው ፡ ደስ ፡ ይለዋል ።
ምድርን ፡ ያያል ፡ እንድትንቀጠቀጥም ፡ ያደርጋል ፡ ፴፪
ተራሮችን ፡ ይዳስሳል ፡ ይጤሳሉም ።

፴፫ እሴብሖ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በሕይወትየ ።
፴፬ ወእዜምር ፡ ለአምላኪየ ፡ በአምጣነ ፡ ሀሎኩ ።
ወአሠምሮ ፡ በቃልየ ።
ወአንሰ ፡ እትፌሣሕ ፡ በእግዚአብሔር ።
፴፭ ወየኅልቁ ፡ ኃጥአን ፡ እምድር ። ወዐማፅያንኒ ፡
ኢይሄልዉ ፡ እንከ ።
ትባርኮ ፡ ነፍስየ ፡ ለእግዚአብሔር ።

መዝሙር ፡ ፻፬ ።
በእንተ ትሩፋን ።

፩ ግነዩ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ወጸውዑ ፡ ስሞ ።
ወንግርዎሙ ፡ ለአሕዛብ ፡ ምግባሮ ።
፪ ሰብሑ ፡ ወዘምሩ ፡ ሎቱ ። ወንግሩ ፡ ኵሎ ፡ መንክሮ ።
፫ ወትከብሩ ፡ በስሙ ፡ ቅዱስ ።
ለይትፌሣሕ ፡ ልብ ፡ ዘየኀሥሥ ፡ ለእግዚአብሔር ።
፬ ኅሥዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ወትጸንዑ ።
ወኅሡ ፡ ገጾ ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ።
፭ ወተዘከሩ ፡ መንክሮ ፡ ዘገብረ ፡
ተአምሪሁ ፡ ወኵነኔ ፡ አፉሁ ።
፮ ዘርዐ ፡ አብርሃም ፡ አግብርቲሁ ። ወደቂቀ ፡ ያዕቆብ ፡
ኅሩያኒሁ ።
፯ ውእቱ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክነ ።
ውስተ ፡ ኵሉ ፡ ምድር ፡ ኵነኔሁ ።
ወተዘከረ ፡ ሥርዐቶ ፡ ዘለዓለም ።
፰ ቃሎ ፡ ዘአዘዘ ፡ ለዐሠርቱ ፡ ምእት ፡ ትውልድ ።
፱ ዘሠርዐ ፡ ለአብርሃም ። ወመሐለ ፡ ለይስሐቅ ።
ወአቀመ ፡ ስምዐ ፡ ለያዕቆብ ።
፲ ወለእስራኤል ፡ ኪዳኖ ፡ ዘለዓለም ።
ወይቤሎ ፡ ለከ ፡ እሁበከ ፡ ምድረ ፡ ከነዓን ።

፲፩ ትኩንክሙ ፡ ሐብለ ፡ ርስትክ ።
፲፪ እንዘ ፡ ውሑዳን፡ ጥቀ፡እሙንቱ።ወፈላስያን፡ውስቴታ።
፲፫ ወኃለፉ ፡ እምሕዝብ ፡ ውስተ ፡ ሕዝብ ።
ወእምንግሥት ፡ ውስተ ፡ ካልዕ ፡ ሕዝብ ።
፲፬ ወኢኀደገ ፡ ይስሐጦሙ ፡ ሰብእ ።
ወገሠጸ ፡ ነገሥተ ፡ በእንቲአሆሙ ።
፲፭ ወኢትግሥሥዎሙ ፡ መሢሓንየ ።
ወኢታሕሥሙ ፡ ዲበ ፡ ነቢያትየ ።
፲፮ ወአምጽአ ፡ ረኃበ ፡ ለብሔር ። ወአጥፍአ ፡ ኵሎ ፡
ኃይለ ፡ እክል ።
፲፯ ፈነወ ፡ ብእሴ ፡ ቅድሜሆሙ ።
ተሠይጠ ፡ ዮሴፍ ፡ ወኮነ ፡ ገብረ ።
፲፰ ወሐሞ ፡ እገሪሁ ፡ በመዋቅሕት ።
ወአምሰጠት ፡ ነፍሱ ፡ እምሐጺን ።
፲፱ ዘእንበለ ፡ ይብጻሕ ፡ ቃሉ ።
ቃለ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምከሮ ።
፳ ፈነወ ፡ ንጉሥ ፡ ወፈትሖ ። ወሜሞ፡ መልአከ፡ አሕዛብ።
፳፩ ወረሰዮ ፡ እግዚአ ፡ ለቤቱ ።
ወአኰነኖ ፡ ላዕለ ፡ ኵሉ ፡ ጥሪቱ ።
፳፪ ከመ ፡ ይገሥጾሙ ፡ ለመላእክቲሁ ፡ ከማሁ ።
ወከመ ፡ ያጥብቦሙ ፡ ለሊቃውንቲሁ ፡ ከማሁ ።
፳፫ ወቦአ ፡ እስራኤል ፡ ብሔረ ፡ ግብጽ ።
ወያዕቆብኒ ፡ ኀደረ ፡ ምድረ ፡ ካም ።
፳፬ ወአብዝኆሙ ፡ ለሕዝቡ ፡ ፈድፋደ ።
ወአጽንዖሙ ፡ እምፀሮሙ ።
፳፭ ወሜጠ ፡ ልቦሙ ፡ ከመ ፡ ይጽልኡ ፡ ሕዝቦ ።
ወከመ ፡ የሐብልይዎሙ ፡ ለአግብርቲሁ ።



በሕይወቴ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እቀኛለሁ ፡ ፴፫
ለአምላኬም፡በምኖርበት፡ ዘመን፡ ሁሉ፡እዘምራለሁ ።
ቃሉ ፡ ለእርሱ ፡ ይጣፍጠው ፡ ፴፬
እኔም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ይለኛል ።
ኃጥአን ፡ ከምድር ፡ ይጥፉ ፡ ፴፭
ዓመፀኞች ፡ እንግዲህ ፡ አይገኙ ።
ነፍሴ፡ሆይ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ባርኪ ። ሃሌ ፡ ሉያ ።

መዝሙር ፡ ፻፬ ።
ስለ ፡ ትሩፋን ።

ሃሌ ፡ ሉያ ።
እግዚአብሔርን፡አመስግኑ ፡ ስሙንም ፡ ጥሩ ፡ ፩
ለአሕዛብም ፡ ሥራውን ፡ ንገሩ ።
ተቀኙለት ፡ ዘምሩለት ፡ ፪
ተአምራቱንም ፡ ሁሉ ፡ ተናገሩ ።
በቅዱስ ፡ ስሙ ፡ ተጓደዱ ፡ ፫
እግዚአብሔርን ፡ የሚፈልግ ፡ ልብ ፡ ደስ ፡ ይበለው ።
እግዚአብሔርን ፡ ፈልጉት ፡ ትጸናላችሁም ፡ ፬
ሁል ፡ ጊዜ ፡ ፊቱን ፡ ፈልጉ ።
ባሮቹ ፡ የአብርሃም ፡ ዘር ፡ ፭
ለእርሱም ፡ የተመረጣችሁ ፡ የያዕቆብ ፡ ልጆች ፡ ሆይ ።
የሠራትን ፡ ድንቅ ፡ ተአምራቱንም ፡ ፮
የፍዱንም ፡ ነገር ፡ አስቡ ።
እርሱ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላካችን ፡ ነው ፡ ፯
ፍርዱ ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ነው ።
ለአብርሃም ፡ ያደረገውን ፡ ለይስሐቅም ፡ የማለውን ። ፰
እስከ ፡ ሺህ ፡ ትውልድም ፡ ያዘዘውን ፡ ቃል ፡ ፱
ኪዳኑን ፡ ለዘላለም ፡ አሰበ ።
የርስታችሁ ፡ ገመድ ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ ፲
ለአንተ ፡ የከነዓንን ፡ ምድር ፡ እሰጣለሁ ፡ ብሎ ።

በቁጥር ፡ ጥቂቶች ፡ እጅግም ፡ ጥቂቶች ፡ ፲፩
በእርሷም ፡ ስደተኞች ፡ በሆኑ ፡ ጊዜ ።
ለእሥራኤል ፡ የዘላለም ፡ ኪዳንን ፡ ፲፪
ለያዕቆብም ፡ ሕግ ፡ የሆነውን ፡ አቆመ ።
ከሕዝብ ፡ ወደ ፡ ሕዝብ ። ፲፫
ከመንግሥትም ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ሕዝብ ፡ አለፉ ።
የቀባኋቸውን ፡ አትዳስሱ ፡ ፲፬
በነቢያቴም ፡ ክፉ ፡ አታድርጉ ፡ ብሎ ።
ሰው ፡ ግፍ ፡ ያደርግባቸው ፡ ዘንድ ፡ አልፈቀደም ፡ ፲፭
ስለ ፡ እነርሱም ፡ ነገሥታትን ፡ ገሠጸ ።
በምድር ፡ ላይ ፡ ራብን ፡ ጠራ ፡ ፲፮
የእህልን ፡ ጕልበት ፡ ሁሉ ፡ ሰበረ ።
በፊታቸው ፡ ሰውን ፡ ላከ ፡ ፲፯
ዮሴፍ ፡ ለባርነት ፡ ተሸጠ ።
እግሮቹም ፡ በእግር ፡ ብረት ፡ ደከሙ ፡ ፲፰
እርሱም ፡ በብረት ፡ ውስጥ ፡ ገባ ።
ቃሉ ፡ እስኪመጣለት ፡ ድረስ ፡ ፲፱
የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ፈተነው ።
ንጉሥ ፡ ላከ ፡ ፈታውም ፡ ፳
የአሕዛብም ፡ አለቃ ፡ አስፈታው ።
አለቆቹን ፡ እንደ ፡ ፈቃዱ ፡ ይገስጽ ፡ ዘንድ ፡ ፳፩
ሽማግሌዎችንም ፡ ጥበበኞች ፡ ያደርጋቸው ፡ ዘንድ ።
የቤቱ ፡ ጌታ ፡ የንብረቱም ፡ ሁሉ፡ አዛዥ፡አደረገው ፳፪
እስራኤልም ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ ገባ ፡ ፳፫
ያዕቆብም ፡ በካም ፡ አገር ፡ አደረ ።
ሕዝቡንም ፡ እጅግ ፡ አበዛ ፡ ፳፬
ከጠላቶቻቸውም ፡ ይልቅ ፡ አበረታቸው ።
ሕዝቡን ፡ ይጠሉ ፡ ዘንድ ፡ ፳፭
በባሮቹም፡ ላይ፡ይተነኰሉ፡ ዘንድ፡ ልባቸውን፡ ለወጠ ።

፳፮ ፈነወ ፡ ሙሴሃ ፡ ገብሮ ። ወአሮንሃ ፡ ኅሩዮ ።
፳፯ ወሤመ ፡ ቃለ ፡ ትእምርት ፡ ላዕሌሆሙ ።
ወመንክርሂ ፡ በምድረ ፡ ካም ።
፳፰ ፈነወ ፡ ጽልመተ ፡ ወአጽለሞሙ ።
ወአምረርዎ ፡ ለቃሉ ።
፳፱ ወረሰየ ፡ ማዮሙ ፡ ደመ ። ወቀተለ ፡ ዓሣቲሆሙ ።
፴ ወአውፅአት ፡ ምድሮሙ ፡ ቈርነናዓተ ።
ውስተ ፡ አብያተ ፡ ነገሥቶሙ ።
፴፩ ይቤ ፡ ወመጽአ ፡ ዐኰት ።
ወትንንያ ፡ ውስተ ፡ ኵሉ ፡ ምድሮሙ ።
፴፪ ወረሰየ ዝናሞሙ በረደ ። ወነደ እሳት ውስተ ምድሮሙ ።
፴፫ ወቀተለ ፡ ወይኖሙ ፡ ወበለሶሙ ።
ወቀጥቀጠ ፡ ኵሎ ፡ ዕፀወ ፡ ብሔሮሙ ።
፴፬ ይቤ ፡ ወመጽአ ፡ አንበጣ ። ወደጎብያ ፡ ዘአልቦ ፡
ኍልቍ ።
፴፭ ወበልዐ ፡ ኵሎ ፡ ፍሬ ፡ ምድሮሙ ።
፴፮ ወቀተለ ፡ ኵሎ ፡ በኵረ ፡ ብሔሮሙ ።
ወቀዳሜ ፡ ኵሉ ፡ ተግባሮሙ ።
፴፯ ወአውፅአሙ ፡ በወርቅ ፡ ወበብሩር ።
ወአልቦ ፡ ደዌ ፡ ውስተ ፡ ሕዝቦሙ ።
፴፰ ወተፈሥሐ ፡ ግብጽ ፡ በፀአቶሙ ። እስመ ፡ ፈርሀዎሙ ።
፴፱ አንጦልዐ ፡ ደመና ፡ ወሠወሮሙ ።
ወእሳተኒ ፡ ከመ ፡ ያብርህ ፡ ሎሙ ፡ በሌሊት ።
፵ ሰአሉ ፡ ወመጽአ ፡ ፍርፍርት ።
ወአጽገቦሙ ፡ ኅብስተ ፡ ሰማይ ።
፵፩ አንቅዐ ፡ ኰኵሐ ፡ ወአውኀዘ ፡ ማየ ።
ወሐሩ ፡ ውስተ ፡ አፍላግ ፡ በድው ።
፵፪ እስመ ፡ ተዘከረ ፡ ቃሎ ፡ ቅዱሰ ። ዘኀበ ፡ አብርሃም ፡ ገብሩ ።
፵፫ ወአውፅአሙ ፡ ለሕዝቡ ፡ በትፍሥሕት ።
ወለኅሩያኒሁ ፡ በሐሤት ።
ወወሀቦሙ ፡ በሐውርተ ፡ አሕዛብ ።
ወወረሱ ፡ ፃማ ፡ ባዕድ ።
፵፬ ከመ ፡ ይዕቀቡ ፡ ሕጎ ። ወይሕሡ ፡ ሥርዐቶ ።

መዝሙር ፡ ፻፭ ።

በእንተ ፡ ትሩፋት ።

፩ ሃሌ ፡ ሉያ ፤
ግነዩ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እስመ ፡ ኄር ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፪ መኑ ፡ ይነግር ፡ ኀይለ ፡ እግዚአብሔር ።
ወይገብር ፡ ከመ ፡ ይስማዕ ፡ ኵሎ ፡ ስብሐቲሁ ።
፫ ብፁዓን ፡ እለ ፡ የዐቅቡ ፡ ፍትሐ ።
ወይገብሩ ፡ ጽድቀ ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ።
፬ ተዘከረነ ፡ እግዚኦ ፡ በሣህልከ ፡ ሕዝበከ ።
ወተሣሀለነ ፡ በአድኅኖትከ ።
፭ ከመ ፡ ንርአይ ፡ ሠናይቶሙ ፡ ለኅሩያኒከ ።
ወከመ ፡ ንትፈሣሕ ፡ በፍሥሓ ፡ ሕዝብከ ።
ወከመ ፡ ንክበር ፡ ምስለ ፡ ርስትከ ።
፮ አበስነ ፡ ምስለ ፡ አበዊነ ። ዐመፅነሂ ፡ ወጌገይነ ።
፯ ወአበዊነሂ ፡ በብሔረ ፡ ግብጽ ፡ ኢያእመሩ ፡ መንክረከ ።
ወኢተዘከሩ ፡ ብዝኀ ፡ ምሕረትከ ።
ወአምረሩከ ፡ እመ ፡ የዐርጉ ፡ ባሕረ ፡ ኤርትራ ።
ወአድኅኖሙ ፡ በእንተ ፡ ስሙ ።



ባሪያውን ፡ ሙሴን ፡ ፳፮
የመረጠውንም ፡ አሮንን ፡ ላከ ።
የተአምራቱን ፡ ነገር ፡ በላያቸው ፡ ፳፯
ድንቁንም ፡ በካም ፡ አገር ፡ አደረገ ።
ጨለማን ፡ ላከ ፡ ጨለመባቸውም ፡ ፳፰
በቃሉም ፡ ዐመፁ ።
ውኃቸውን ፡ ወደ ፡ ደም ፡ ለወጠ ፡ ፳፱
ዓሦቻቸውንም ፡ ገደለ ።
ምድራቸውና ፡ የንጉሦቻቸውም ፡ ቤቶች ፡ ፴
በጓጕንቸር ፡ ተሞሉ ።
ተናገረ ፡ የውሻ ፡ ዝንብ ፡ ፴፩
ትንኝም ፡ በዳርቻቸው ፡ መጡ ።
ዝናማቸውን ፡ በረዶ ፡ አደረገው ፡ ፴፪
እሳትም ፡ በምድራቸው ፡ ተቃጠለች ።
ወይናቸውንና ፡ በለሳቸውን ፡ መታ ፡ ፴፫
የአገራቸውንም ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ ፡ ሰበረ ።
ተናገረ ፡ አንበጣም ፡ ፴፬
ስፍር ፡ ቍጥር ፡ የሌለውም ፡ ኩብኩባ ፡ መጣ ።
የአገራቸውንም ፡ ለምለም ፡ ሁሉ ፡ አጠፉ ፡ ፴፭
የምድራቸውንም ፡ ፍሬ ፡ በላ ።
የአገራቸውንም ፡ በኵር ፡ ሁሉ ፡ ፴፮
የኃይላቸውን ፡ መጀመሪያ ፡ ሁሉ ፡ መታ ።
በወርቅና ፡ በብርም ፡ አወጣቸው ፡ ፴፯
በወገናቸውም ፡ ውስጥ ፡ ደዌ ፡ አልነበረም ።
ፈርተዋቸው ፡ ነበርና ፡ ፴፰
ግብጽ ፡ በመውጣታቸው ፡ ደስ ፡ አላት ።
ደመናን ፡ ለመሸፈኛ ፡ ዘረጋላቸው ፡ ፴፱
እሳትንም ፡ በሌሊት ፡ ያበራላቸው ፡ ዘንድ ፡ ዘረጋ ።
ለመኑ ፡ ድርጭትንም ፡ አመጣላቸው ፡ ፵
የሰማይንም ፡ እንጀራ ፡ አጠገባቸው ።

ለባሪያው ፡ ለአብርሃም ፡ የነገረውን ፡ ፵፩
ቅዱስ ፡ ቃሉን ፡ አስቦአልና ።
ዓለቱን ፡ ሰነጠቀ ፤ ውኃውንም ፡ አፈሰሰ ፡ ፵፪
ወንዞች ፡ በበረሃ ፡ ሄዱ ።
ሕዝቡንም ፡ በደስታ ፤ ፵፫
የተመረጡትንም ፡ በእልልታ ፡ አወጣ ።
ሕጉን ፡ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ፤ ፵፬
ሥርዓቱንም ፡ ይፈልጉ ፡ ዘንድ ።
የአሕዛብን ፡ አገሮች ፡ ሰጣቸው ። ፵፭
የአሕዛብንም ፡ ድካም ፡ ወረሱ ፤ ሃሌ ፡ ሉያ ።

መዝሙር ፡ ፻፭ ።
ስለ ፡ ትሩፋን ።

ሃሌ ፡ ሉያ ፤
ቸር ፡ ነውና ፡ ምሕረቱም ፡ ለዘለዓለም ፡ ነውና ፡ ፩
እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ።
የእግዚአብሔርን ፡ ኃይል ፡ ማን ፡ ይናገራል ? ፪
ምስጋናውንስ ፡ ማን ፡ ያሰማል ?
ፍርድን ፡ የሚጠብቁ ፡ ፫
ጽድቅንም ሁል ፡ ጊዜ ፡ የሚያደርጉ ፡ ምስጉኖች ፡ ናቸው ።
የመረጥሃቸውን ፡ በጎነት ፡ እናይ ፡ ዘንድ ፡ ፬
በሕዝብህም ፡ ደስታ ፡ ደስ ፡ ይለን ፡ ዘንድ ፡
ከርስትህም ፡ ጋራ ፡ እንኳደድ ፡ ዘንድ ።
አቤቱ ፡ በሕዝብህ ፡ ሞገስ ፡ አስበን ፡ ፭
በመድኃኒትህም ፡ ጐብኘን ።
ከአባቶቻችን ፡ ጋራ ፡ ኀጢአት ፡ ሠራን ፡ ፮
ዓመፅንም ፡ በደልንም ።
አባቶቻችን ፡ በግብጽ ፡ ሳሉ ፡ ተአምራትህን ፡ አላስተዋሉም ፤ ፯
የምሕረትህንም ፡ ብዛት ፡ አላሰቡም ፡
በኤርትራ ፡ ባሕር ፡ በአለፉ ፡ ጊዜ ፡ ዐመፁብህ ።

፰ ከመ ፡ ያርእዮሙ ፡ ኀይሎ ።
፱ ወገሠፆ ፡ ለባሕረ ፡ ኤርትራ ፡ ወየብሰት ።
ወመርሖሙ ፡ በቀላይ ፡ ከመ ፡ ዘበገዳም ።
፲ ወአድኀኖሙ ፡ እምእደ ፡ ጸላእቶሙ ።
ወአንገፎሙ ፡ እምእደ ፡ ጸሮሙ ።
፲፩ ወደፈኖሙ ፡ ማይ ፡ ለእለ ፡ ሮድዎሙ ።
ወኢተርፈ ፡ አሐዱ ፡ እምውስቴቶሙ ።
፲፪ ወተአመኑ ፡ በቃሉ ። ወሰብሕዎ ፡ በስብሐቲሁ ።
፲፫ ወአፍጠኑ ፡ ረሲዐ ፡ ምግባሩ ።
ወኢተዐገሡ ፡ በምክሩ ።
፲፬ ወፈተዉ ፡ ፍትወተ ፡ በገዳም ።
ወአምረርዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በበድው ።
፲፭ ወወሀቦሙ ፡ ዘሰአሉ ። ፈነወ ፡ ጽጋበ ፡ ለነፍሶሙ ።
፲፮ ወአምዕዕዎ ፡ ለሙሴ ፡ በትዕይንት ።
ወለአሮን ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ።
፲፯ አብቀወት ፡ ምድር ፡ ወውኅጦቶ ፡ ለዳታን ።
ወደፈነቶሙ ፡ ለተዓይኒ ፡ አቤሮን ።
፲፰ ወነደ ፡ እሳት ፡ ውስተ ፡ ተዓይኒሆሙ ።
ወአውዐዮሙ ፡ ነበልባል ፡ ለኃጥኣን ።
፲፱ ወገብሩ ፡ ላሕመ ፡ በኮሬብ ። ወሰገዱ ፡ ለግልፎ ።
ወወለጡ ፡ ክብሮሙ ።
፳ በአምሳለ ፡ ላህም ፡ ዘይትረዐይ ፡ ሣዕረ ።
ወረስዕዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ዘአድኀኖሙ ።
፳፩ ዘገብረ ፡ ዐቢያተ ፡ በግብጽ ።
፳፪ ወመንክረ ፡ በምድረ ፡ ካም ።
ወግሩመ ፡ በባሕረ ፡ ኤርትራ ።
፳፫ ወይቤ ፡ ከመ ፡ ይሰርዎሙ ።
ሶበ ፡ አኮ ፡ ሙሴ ፡ ኅሩዩ ። ቆመ ፡ ቅድሜሁ ፡ አመ ፡
ብድብድ ።
ከመ ፡ ይሚጥ ፡ መቅሠፍቶ ፡ መዓቱ ።
ወከመ ፡ ኢይሥርዎሙ ።
፳፬ ወመነኑ ፡ ምድረ ፡ መፍትወ ። ወኢተአመኑ ፡ በቃሉ።
፳፭ ወአንጐርጐሩ ፡ በውስተ ፡ ተዓይኒሆሙ ።
ወኢሰምዑ ፡ ቃለ ፡ እግዚአብሔር ።
ወአንሥአ ፡ እዴሁ ፡ ላዕሌሆሙ ።
፳፮ ከመ ፡ ይንጽኆሙ ፡ በገዳም ።
ወከመ ፡ ይንፃኅ ፡ ዘርዖሙ ፡ ውስተ ፡ አሕዛብ ።
፳፯ ወከመ ፡ ይዝርዎሙ ፡ ውስተ ፡ በሐውርት ።
፳፰ ወተፈፅሙ ፡ በብዔል ፡ ፌጎር ።
ወበልዑ ፡ መሥዋዕተ ፡ ምዉት ።
፳፱ ወወሐክዎ ፡ በምግባሪሆሙ ።
ወበዝኀ ፡ ብድብድ ፡ ላዕሌሆሙ ።
፴ ተንሥአ ፡ ፊንሐስ ፡ ወአድኃኖሙ ።
፴፩ ኀደገ ፡ ብድብድ ፡ ወተኈለቈ ፡ ጽድቀ ።
ለትውልደ ፡ ትውልድ ፡ እስከ ፡ ለዓለም ።
፴፪ ወአምዕዕዎ ፡ በኀበ ፡ ማየ ፡ ቅስት ።
፴፫ ወሐመ ፡ ሙሴ ፡ በእንቲአሆሙ ።
እስመ ፡ አምረርዎ ፡ ለነፍሱ ። ወአዘዘ ፡ በከናፍሪሁ ።
፴፬ ወኢሠረዉ ፡ አሕዛበ ፡ ዘይቤሎሙ ፡ እግዚአብሔር ።
፴፭ ወተደመሩ ፡ ምስለ ፡ አሕዛብ ።
ወተምህሩ ፡ ምግባሮሙ ።
፴፮ ወተቀንዩ ፡ ለግልፎሆሙ ። ወኮኖሙ ፡ ጌጋየ ።
፴፯ ዘብሖ ፡ ደቂቆሙ ፡ ወአዋልዲሆሙ ፡ ለአጋንንት ።
ወከዐዉ ፡ ደመ ፡ ንጹሐ ።



ኀይሉንም ፡ ለማስታወቅ ፡ ፰
ስለ ፡ ስሙ ፡ አዳናቸው ።
የኤርትራንም ፡ ባሕር ፡ ገሠጸ ፡ እርሱም ፡ ደረቀ ፡ ፱
እንደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ በጥልቅ ፡ መራቸው ።
ከሚጠሏቸውም ፡ እጅ ፡ አዳናቸው ፡ ፲
ከጠላትም ፡ እጅ ፡ ተቤዣቸው ።
የሚያሳድዷቸውንም ፡ ውኃ ፡ ደፈናቸው ፡ ፲፩
ከእነርሱም ፡ አንድ ፡ ስንኳ ፡ አልቀረም ።
በቃሉም ፡ አመኑ ፡ ፲፪
ምስጋናውንም ፡ ዘመሩ ።
ፈጥነውም ፡ ሥራውን ፡ ረሱ ፡ ፲፫
በምክሩም ፡ አልታገሡም ።
በምድረ ፡ በዳም ፡ ምኞትን ፡ ተመኙ ፡ ፲፬
በበረሃም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ተፈታተኑት ።
የለመኑትንም ፡ ሰጣቸው ፡ ፲፭
ለነፍሳቸው ፡ ግን ፡ ክሳትን ፡ ላከ ።
ሙሴንም ፡ እግዚአብሔር ፡ የቀደሰውንም ፡ አሮንን ፡ ፲፮
በሰፈር ፡ ተመቀኟቸው ።
ምድርም ፡ ተከፈተች ፡ ዳታንንም ፡ ዋጠችው ፡ ፲፯
የአቤሮንንም ፡ ወገን ፡ ደፈነች ።
በማኅበራቸውም ፡ እሳት ፡ ነደደች ፡ ፲፰
ነበልባልም ፡ ኃጥኣንን ፡ አቃጠላቸው ።
በኮሬብም ፡ የጥጃ ፡ ጣዖት ፡ ሠሩ ፡ ፲፱
ለጣዖትም ፡ ሰገዱ ።
ሣርም ፡ በሚበላ ፡ በበሬ ፡ ምሳሌ ፡ ፳
ክብራቸውን ፡ ለወጡ ።
ጽድቅን ፡ በካም ፡ ምድር ፡ ፳፩
ግሩም ፡ ነገርንም ፡ በኤርትራ ፡ ባሕር ፡
ታላቅ ፡ ነገርንም ፡ በግብጽ ፡ ያደረገውን ፡ ፳፪
ያዳናቸውንም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ረሱ ።

እንዳያጠፋቸው ፡ ቍጣውን ፡ ይመልስ ፡ ዘንድ ፡ ፳፫
የተመረጠው ፡ ሙሴ ፡ በመቅሠፍት ፡ ጊዜ ፡ በፊቱ ፡ ባይቆም ፡ ኖሮ ፤
ያጠፋቸው ፡ ዘንድ ፡ በወደደ ፡ ነበር ።
የተወደደችውን ፡ ምድር ፡ ናቁ ፡ ፳፬
በቃሉም ፡ አልታመኑም ።
በድንኳኖቻቸውም ፡ ውስጥ ፡ አንጐራጐሩ ፡ ፳፭
የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ አልሰሙም ።
በምድረ ፡ በዳም ፡ ይጥላቸው ፡ ዘንድ ፡ ፳፮
ዘራቸውንም ፡ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ ይዘራ ፡ ዘንድ ።
በያገሩም ፡ ይበትናቸው ፡ ዘንድ ፡ ፳፯
እጁን ፡ አነሣባቸው ።
በብዔል ፡ ፌጎርም ፡ ተገናኙ ፡ ፳፰
የሙታንንም ፡ መሥዋዕት ፡ በሉ ።
በሥራቸውም ፡ አስመረሩት ፡ ፳፱
ቸነፈርም ፡ በላያቸው ፡ በዛ ።
ፊንሐስም ፡ ተነሥቶ ፡ ፈረደባቸው ፡ ፴
ቸነፈሩም ፡ ተወ ።
ያም ፡ ጽድቅ ፡ ፴፩
እስከ ፡ ዘላለም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ተቆጠረለት ።
በክርክር ፡ ውሃ ፡ ዘንድም ፡ አስቆጡት ። ፴፪
መንፈሱን ፡ አሳዝነዋልና ።
ስለ ፡ እነርሱም ፡ ሙሴ ፡ ተበሳጨ ፡ ፴፫
በከንፈሮቹም ፡ በስንፍና ፡ ተናገረ ።
እግዚአብሔርም ፡ እንዳላቸው ፡ አሕዛብን ፡ አላጠፉም ፡ ፴፬
ከአሕዛብም ፡ ጋራ ፡ ተደባለቁ ፡ ሥራቸውንም ፡ ተማሩ ፡ ፴፭
ለጣዖቶቻቸውም ፡ ተገዙ ፡ ወጥመድም ፡ ሆኑባቸው ፡ ፴፮
ወንዶች ፡ ልጆቻቸውንና ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻቸውን ፡ ፴፯
ለአጋንንት ፡ ሠዉ ፡

፴፰ ደመ ፡ ደቂቆሙ ፡ ወአዋልዲሆሙ ።
ወሦዑ ፡ ለግልፎ ፡ ከነዓን ።
ወተቀትለት ፡ ምድር ፡ በደም ።
፴፱ ወረኵሰት ፡ ምድር ፡ በምግባሪሆሙ ።
ወዘመዉ ፡ በጣዖቶሙ ።
፵ ወተምዐ ፡ እግዚአብሔር ፡ መዓተ ፡ ላዕለ ፡ ሕዝቡ ።
ወአስቆረሮሙ ፡ ለርስቱ ።
፵፩ ወአግብኦሙ ፡ ውስተ ፡ እደ ፡ ፀሮሙ ።
፵፪ ወቀነይዎሙ ፡ ጸላእቶሙ ። ወአሕመምዎሙ ፡ ፀሮሙ ።
ወኀስሩ ፡ በታሕተ ፡ እደዊሆሙ ።
፵፫ ወዘልፈ ፡ ያድኅኖሙ ።
እሙንቱሰ ፡ አምረርዎ ፡ በምክሮሙ ።
ወሐሙ ፡ በኃጢአቶሙ ።
፵፬ ወርእዮሙ ፡ ከመ ፡ ተመንደቡ ።
፵፭ ወሰምዖሙ ፡ ጸሎቶሙ ። ወተዘከረ ፡ ኪዳኖ ።
ወነስሐ ፡ በከመ ፡ ብዝኀ ፡ ምሕረቱ ።
ወወሀቦሙ ፡ ሣህሎ ።
፵፮ በቅድመ ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ ፄወውዎሙ ።
፵፯ አድኅነነ ፡ እግዚኦ ፡ አምላክነ ።
ወአስተጋብአነ ፡ እምአሕዛብ ።
ከመ ፡ ንግነይ ፡ ለስምከ ፡ ቅዱስ ።
ወከመ ፡ ንትመካህ ፡ በስብሐቲከ ።
ይትባረክ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላከ ፡ እስራኤል ።
፵፰ እምቅድመ ፡ ዓለም ፡ ወእስከ ፡ ለዓለም ።
ለይበል ፡ ኵሉ ፡ ሕዝብ ፡ ለይኩን ፡ ለይኩን ።

መዝሙር ፡ ፻፮ ።

በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ ግነዩ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እስመ ፡ ኄር ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።

፪ ለይበሉ ፡ እለ ፡ አድኃኖሙ ፡ እግዚአብሔር ።
እለ ፡ አድኃኖሙ ፡ እምእደ ፡ ፀሮሙ ።
ወአስተጋብአሙ ፡ እምበሓውርት ።
፫ እምጽባሕ ፡ ወእምዐረብ ፡ ወመስዕ ፡ ወባሕር
፬ ወሳኰዩ ፡ ውስተ ፡ በድው ፡ ዘአልቦ ፡ ማይ ።
ወኢረከቡ ፡ ፍኖተ ፡ ሀገረ ፡ ብሔሮሙ ።
፭ ጽምኡ ፡ ወርኅቡ ፡ ወኀልቀት ፡ ነፍሶሙ ፡ ባላዕሌሆሙ
፮ ወአውየዉ ፡ ኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሶበ ፡ ተመንደቡ ፡
ወአድኅኖሙ ፡ እምንዳቤሆሙ ።
፯ ወመርሖሙ ፡ ፍኖተ ፡ ርቱዐ ። ከመ ፡ ይሑሩ ፡ ፍኖተ ፡ ሀገሮሙ ።
ንግሩ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ምሕረቶ ።
፰ ወመንክሮሂ ፡ ለዕጓለ ፡ እመሕያው ።
፱ እስመ ፡ አጽገበ ፡ ነፍሰ ፡ ርኅብተ ።
ወመልዓ ፡ ለነፍስ ፡ ዕራቃ ፡ በረከተ ።
፲ ለእለ ፡ ይነብሩ ፡ ውስተ ፡ ጽልመት ፡ ወጽላሎተ ፡ ሞት።
ወሙቁሓን ፡ በንዴት ፡ ወበሐጺን ።
፲፩ እስመ ፡ አምረሩ ፡ ቃለ ፡ እግዚአብሔር ።
፲፪ ወአምዐዑ፡ምክረ፡ልዑል።ወሠርሐ፡በሕማም፡ልቦሙ ።
ደወዩ ፡ ወኀጥኡ ፡ ዘይቀብሮሙ ።
፲፫ ወአውየዉ ፡ ኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሶበ ፡ ተመንደቡ ።
ወአድኅኖሙ ፡ እምንዳቤሆሙ ።
፲፬ ወአውፅኦሙ ፡ እምጽልመት ፡ ወጽላሎተ ፡ ሞት ።
ወሰበረ ፡ መዋቅሕቲሆሙ ።
ንግሩ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ምሕረቶ ።
፲፭ ወመንክሮሂ ፡ ለዕጓለ ፡ እመሕያው ።
እስመ ፡ ሰበረ ፡ ኆኃተ ፡ ብርት ።
፲፮ ወቀጥቀጠ ፡ መናሥግተ ፡ ዘሐፂን ።



የወንዶች፡ልጆቻቸውንና፡የሴቶች፡ልጆቻቸውን፡ደም፡ ፴፰
ለከነዓን፡ጣዖቶች፡የሠዉዋቸውን፡ንጹሕ፡ደም፡አፈሰሱ ።
ምድርም ፡ በደም ፡ ረከሰች ።
በሥራቸውም ፡ ረከሱ ፡ ፴፱
በማድረጋቸውም ፡ አመነዘሩ ።
የእግዚአብሔርም ፡ ቍጣ ፡ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ ነደደ ፡ ፵
ርስቱንም ፡ ተጸየፈ ።
ወደ ፡ አሕዛብም ፡ እጅ ፡ አሳለፋቸው ፡ ፵፩
የሚጠሏቸውም ፡ ገዟቸው ።
ጠላቶቻቸውም ፡ ግፍ ፡ አደረጉባቸው ፡ ፵፪
ከእጃቸውም ፡ በታች ፡ ተዋረዱ ።
ብዙ ፡ ጊዜ ፡ አዳናቸው ፡ ፵፫
ነገር ፡ ግን ፡ በምክራቸው ፡ አስቆጡት ።
በኀጢአታቸውም ፡ ተዋረዱ ።
እርሱም ፡ ጩኸታቸውን ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ፵፬
ጭንቃቸውን ፡ ተመለከተ ።
ለእነርሱም ፡ ኪዳኑን ፡ አሰበ ፡ ፵፭
እንደ ፡ ምሕረቱም ፡ ብዛት ፡ አዘነላቸው ።
በማረኳቸውም ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ሞገስን ፡ ሰጣቸው ፡ ፵፮
አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፡ አድነን ፡ ፵፯
ቅዱስ ፡ ስምህን ፡ እናመሰግን ፡ ዘንድ ።
በምስጋናህም ፡ እንመካ ፡ ዘንድ ።
ከአሕዛብ ፡ መካከል ፡ ሰብስበን ።
ከዘላለም ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ፵፰
የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይባረክ ።
ሕዝብህም ፡ ሁሉ ፡ አሜን ፡ ይበል ። ሃሌ ፡ ሉያ ።

መዝሙር ፡ ፻፮ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

ቸር ፡ ነውና ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ፡ ፩
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።

እግዚአብሔር ፡ ያዳናቸው ፡ ፪
ከጠላቶች ፡ እጅ ፡ ያዳናቸው ፡ ይናገሩ ።
ከምሥራቅና ፡ ከምዕራብ ፤ ከሰሜንና ፡ ከባሕር ፡ ፫
ከያገሩም ፡ ሰበሰባቸው ።
ውሃ ፡ በሌለበት ፡ መንገድ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ተቅበዘበዙ ፡ ፬
የሚኖሩበትም ፡ ከተማ ፡ አላገኙም ።
ተራቡ ፡ ተጠሙም ፡ ፭
ነፍሳቸውም ፡ በውስጣቸው ፡ አለቀች ።
በተጨነቁ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኹ ፤ ፮
ከመከራቸውም ፡ አዳናቸው ።
ወደሚኖሩበት ፡ ከተማ ፡ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፡ ፯
የቀና ፡ መንገድን ፡ መራቸው ።
የተራበችን ፡ ነፍስ ፡ አጥግቧልና ፡ ፰
የተራቆተችውንም ፡ ነፍስ ፡ በበረከት ፡ መልቶአልና ።
ለሰው ፡ ልጆች ፡ ስለ ፡ አደረገው ፡ ተአምራት ፡ ፱
ስለ ፡ ምሕረቱም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመስግኑ ።
በጨለማ ፡ በሞትም ፡ ጥላ ፡ ሥር ፡ የተቀመጡ ፤ ፲
በችጋር ፡ በብረትም ፡ የታሰሩ ።
የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስለ ፡ ዐመፁ ፡
የልዑልንም ፡ ምክር ፡ ስለ ፡ ናቁ ። ፲፩
ልባቸው ፡ በድካም ፡ ተዋረደ ፡ ፲፪
ታመሙ ፡ የሚረዳቸውም ፡ አጡ ።
በተጨነቁ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኹ ፡ ፲፫
ከመከራቸውም ፡ አዳናቸው ።
ከጨለማና ፡ ከሞት ፡ ጥላ ፡ አወጣቸው ፡ ፲፬
እስራታቸውንም ፡ ፈታ ።
የናሱን ፡ ደጆች ፡ ስለ ፡ ሰበረ ፡ ፲፭
የብረቱንም ፡ መወርወሪያ ፡ ስለ ፡ ቆረጠ ።
ለሰው ፡ ልጆች ፡ ስለ ፡ አደረገው ፡ ተአምራት ፡ ፲፮
ስለ ፡ ምሕረቱም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመስግኑ ።

፲፯ ወተወክፎሙ ፡ እምፍኖተ ፡ ጌጋዮሙ ።
እስመ ፡ ሐሙ ፡ በኃጢአቶሙ ።
፲፰ ወክርሖ ፡ መብልዐ ፡ አስቈረረት ፡ ነፍሶሙ ።
ወቀርቡ ፡ ኀበ ፡ አናቅጸ ፡ ሞት ።
፲፱ ወአውየዉ ፡ ኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሶበ ፡ ተመንደቡ ፡
ወአድኀኖሙ ፡ እምንዳቤሆሙ ።
፳ ፈነወ ፡ ቃሎ ፡ ወሐየዎሙ ። ወአድኃኖሙ ፡ እሞቶሙ።
ንግሩ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ምሕረቶ ።
፳፩ ወመንክሮሂ ፡ ለዕጓለ ፡ እመሕያው ።
፳፪ ወይሡዑ ፡ሎቱ ፡ መሥዋዕተ ፡ ስብሐት ።
ወይንግሩ ፡ ግብሮ ፡ በትፍሥሕት ።
፳፫ እለ ፡ ይወርዱ ፡ ውስተ ፡ ባሕር ፡ በአሕማር ።
ወይትጌበሩ ፡ ተግባሮሙ ፡ ውስተ ፡ ማይ ፡ ብዙኅ ።
፳፬ እሙንቱሰ ፡ የአምሩ ፡ ግብረ ፡ እግዚአብሔር ።
ወመንክሮሂ ፡ በውስተ ፡ ልጎት ።
፳፭ ይቤ ፡ ወመጽአ ፡ መንፈሰ ፡ ዐውሎ ።
ወተለዐለ ፡ ማዕበል ።
፳፮ የዐርጉ ፡ እስከ ፡ ሰማይ ።
ወይወርዱ ፡ ውስተ ፡ ቀላይ ።
ወተመስወት ፡ ነፍሶሙ ፡ በሕማም ።
ደንገፁ ፡ ወተሀውኩ ፡ ከመ ፡ ስኩር ።
፳፯ ወተሰጥመ ፡ ኵሉ ፡ ጥበቦሙ ።
፳፰ ወአውየዉ ፡ ኀበ ፡እግዚአብሔር ፡ ሶበ ፡ ተመንደቡ።
ወአድኃኖሙ ፡ እምንዳቤሆሙ ።
፳፱ አጥፍአ ፡ ለዐውሎ ፤ ወአርመመ ፡ ባሕር ። ወአርመመ
ማዕበል ።
፴ ወተፈሥሑ ፡ እስመ ፡ አዕረፉ ።
ወመርሖሙ ፡ ውስተ ፡ መርሶ ፡ ኀበ ፡ ፈቀዱ ።
ንግሩ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ምሕረቶ ።
፴፩ ወመንክሮሂ ፡ ለዕጓለ ፡ እመሕያው ።

፴፪ ወያዐብይዎ ፡ በማኅበረ ፡ አሕዛብ ።
ወይሴብሕዎ ፡ በመንበረ ፡ ሊቃውንት ።
፴፫ ወረሰዮሙ ፡ ለአፍላግ ፡ በድወ ።
ወረሰየ ፡ ምጽማዓ ፡ሙኃዘ ፡ ማይ ።
ወረሰያ ፡ ለምድር ፡ ዔወ ፡ እንተ ፡ ትፈሪ ።
፴፬ በእከዮሙ ፡ ለእለ ፡ ይነብርዋ ።
፴፭ ወረሰዮ ፡ ለበድው ፡ ሙኃዘ ፡ ማይ ።
ወለምድረ ፡ በድው ፡ ቀላያተ ፡ ማያት ።
፴፮ ወአንበረ ፡ ህየ ፡ ርኁባነ ።
ሐነፁ ፡ አኅጉረ ፡ ኀበ ፡ ይነብሩ ።
፴፯ ተከሉ ፡ ወይነ ፡ ወዘርሁ ፡ ገራውኃ ።
ወገብሩ ፡ ማእረረ ፡ እክል ።
፴፰ ባረኮሙ ፡ ወበዝኁ ፡ ፈድፋደ ።
ወኢያውኀደ ፡ ሎሙ ፡ እንስሳሆሙ ።
፴፱ ደወዩ ፡ ወውኅዱ ። በሕማም ፡ እኩይ ፡ ወበጻዕር ።
፵ ወተክዕወ ፡ ኀሣር ፡ዲበ ፡ መላእክት ።
ወአስሐቶሙ ፡ ውስተ ፡ በድው ፡ ዘኢኮነ ፡ ፍኖተ ።
፵፩ ወረድአ ፡ ለነዳይ ፡ በተጽናሱ ።
ወረሰዮ ፡ ከመ ፡ አባግዐ ፡ ብሔር ።
፵፪ ይርአዩ ፡ ራትዓን ፡ ወይትፌሥሑ ።
ወትትፌፀም ፡ አፉሃ ፡ ኵላ ፡ ዐመፃ ።
፵፫ መኑ ፡ ጠቢብ ፡ ዘየዐቅቦ ፡ ለዝ ።
ወየአምር ፡ ከመ ፡ መሐሪ ፡ እግዚአብሔር ።

መዝሙር ፡ ፻፯ ።
በእንተ ፡ ሕዝቅያስ ።
፩ ጥቡዕ ፡ ልብየ ፡ እግዚእ ፡ ጥቡዕ ፡ ልብየ ።
ጥቡዕ ፡ ልብየ ፡ እሴብሕ ፡ ወእዜምር ።
ወይትነሣእ ፡ ክብርየ ።
፪ ወእትነሣእ ፡ በመዝሙር ፡ ወበመሰንቆ ።
ወእትነሣእ ፡ በጽባሕ ።



ስለ ፡ ዓመፃቸው ፡ ሰነፉ ፡ ፲፯
ስለ ፡ ኀጢአታቸውም ፡ ተቸገሩ ።
ሰውነታቸው ፡ መብልን ፡ ሁሉ ፡ ተጸየፈች ፡ ፲፰
ወደ ፡ ሞትም ፡ ደጆች ፡ ቀረቡ ።
በተጨነቁ ፡ ጊዜም ፡ ወደ ፡እግዚአብሔር ፡ ጮኹ ፡ ፲፱
ከመከራቸውም ፡ አዳናቸው ።
ቃሉን ፡ ላከ ፡ ፈወሳቸውም ፡ ፳
ከጥፋታቸውም ፡ አዳናቸው ።
ለሰው ፡ ልጆች ፡ ስለ ፡ አደረገው ፡ ተአምራት ፡ ፳፩
ስለ ፡ ምሕረቱም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመስግኑ ።
የምስጋና ፡ መሥዋዕትንም ፡ ይሠዉለት ። ፳፪
በእልልታም ፡ ሥራውን ፡ ይንገሩ ።
በመርከቦች ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ የሚወርዱ ፡ ፳፫
በታላቅ ፡ ውሃ ፡ ሥራቸውን ፡ የሚሠሩ ።
እነርሱ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሥራ ፡ ፳፬
በጥልቅም ፡ ያለችውን ፡ ድንቁን ፡ አዩ ።
ተናገረ ፤ ዓውሎ ፡ ነፋስም ፡ ተነሣ ፡ ፳፭
ሞገድም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለ ።
ወደ ፡ ሰማይ ፡ ይወጣሉ ፡ ወደ ፡ ጥልቅም ፡ ይወርዳሉ፡ ፳፮
ነፍሳቸውም ፡ በመከራ ፡ ቀለጠች ።
ደነገጡ ፡ እንደሰካርም ፡ ተንገደገዱ ፡ ፳፯
ጥበባቸውም ፡ ሁሉ ፡ ተዋጠች ።
በተጨነቁ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡እግዚአብሔር ፡ ጮሁ፡ ፳፰
ከመከራቸውም ፡ አዳናቸው ።
ዓውሎንም ፡ ጸጥ ፡ አደረገ ፡ ፳፱
ሞገዱም ፡ ዝም ፡ አለ ።
ዝም ፡ ብሎአልና ፡ ደስ ፡ አላቸው ፡ ፴
ወደ ፡ ፈለጉትም ፡ ወደብ ፡ መራቸው ፡
ለሰው ፡ ልጆች ፡ ስለአደረገው ፡ ተአምራት ፡ ፴፩
ስለ ፡ ምሕረቱም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመስግኑ ።

በሕዝብ ፡ ጉባኤ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያድርጉት ፡ ፴፪
በሽማግሎችም ፡ ሸንጎ ፡ ያመስግኑት ።
ወንዞችን ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ፴፫
የውሀውንም ፡ ምንጮች ፡ ደረቅ ፡ አደረጋቸው ።
ከተቀመጡባት ፡ ክፋት ፡ የተነሣ ፡ ፴፬
ፍሬያማዋን ፡ ምድር ፡ ጨው ፡ አደረጋት ።
ምድረ ፡ በዳን ፡ ለውሀ ፡ መቆሚያ ፡ ፴፭
ደረቂንም ፡ ምድር ፡ የውሀ ፡ ምንጮች ፡ አደረገ ።
በዚያም ፡ ራብተኞችን ፡ አስቀመጠ ፡ ፴፮
የሚኖሩበትንም ፡ ከተማ ፡ ሠሩ ።
እርሻዎችንም ፡ ዘሩ ፡ ወይኖችንም ፡ ተከሉ ፡ ፴፯
የእህልንም ፡ ሰብል ፡ ሰበሰቡ ።
ባረካቸውም ፡ እጅግም ፡ በዙ ፡ ፴፰
እንስሶቻቸውንም ፡ አላሳነሰባቸውም ።
እነርሱ ፡ በችግር ፡ በክፋት ፡ በጭንቀት ፡ ተዋረዱ ፡ ፴፱
በአለቆችም ፡ ላይ ፡ ኀሣርን ፡ አፈሰሰ ፡ ፵
መንገድም ፡ በሌለበት ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ አሳታቸው ።
ችጋረኛንም ፡ ከችግሩ ፡ ረዳው ፡ ፵፩
እንደ ፡ በጎች ፡ መንጋ ፡ ወገን ፡ አደረገው ።
ቅኖች ፡ ያያሉ ፡ ደስም ፡ ይላቸዋል ፡ ፵፪
ኃጢአትም ፡ ሁሉ ፡ አፏን ፡ ትዘጋለች ።
ዐዋቂ ፡ የሆነ ፡ ይህን ፡ ይጠብቃል ፡ ፵፫
የእግዚአብሔርንም ፡ ምሕረት ፡ ያስተውላል ።

መዝሙር ፡ ፻፯ ።
ስለ ፡ ሕዝቅያስ ።
ልቤ ፡ጽኑ ፡ ነው ፡ አቤቱ ፡ ልቤ ፡ ጽኑ ፡ ነው ፡ ፩
እቀኛለሁ ፡ በክብሬም ፡ እዘምራለሁ ።
በገና ፡ ሆይ ፡ ተነሣ ፡ መሰንቆም ፡ ተነሣ ፡ ፪
እኔም ፡ ማልጄ ፡ እነሣለሁ ።

፫ እገኒ ፡ ለከ ፡ በውስተ ፡ አሕዛብ ፡ እግዚኦ ።
ወእዜምር ፡ ለከ ፡ በውስተ ፡ ሕዝብ ።
እስመ ፡ ዐብየት ፡ እስከ ፡ ሰማያት ፡ ምሕረትከ ።
፬ ወእስከ ፡ ደመናት ፡ ጽድቅከ ።
፭ ተለዐል ፡ እግዚአብሔር ፡ መልዕልተ ፡ ሰማያት ።
ወበኵሉ ፡ ምድር ፡ ስብሐቲሁ ።
፮ ከመ ፡ ይድኅኑ ፡ ፍቁራኒከ ።
አድኅን ፡ በየማንከ ፡ ወስምዐኒ ።
፯ እግዚአብሔር ፡ ነበበ ፡ በመቅደሱ ።
እትሐሠይ ፡ ወእትከፈል ፡ ሰቂማ ።
ወእሳፈር ፡ እዕጻዳተ ፡ ቈላት ።
፰ ዚአየ ፡ ውእቱ ፡ ገለአድ ፡ ወዚአየ ፡ ምናሴ ።
ወኤፍሬም ፡ ሰዋቀ ፡ ርእስየ ።
ወይሁዳ ፡ ንጉሥየ ።
፱ ወሞዓብ ፡ ካህን ፡ ተስፋየ ።
ዲበ ፡ ኤዶምያስ ፡ እሰፍሕ ፡ መከየድየ ።
ሊተ ፡ ይገንዩ ፡ ኢሎፍሊ ።
፲ መኑ ፡ ይወስደኒ ፡ ሀገረ ፡ ጥቅም ።
ወመኑ ፡ ይመርሐኒ ፡ እስከ ፡ ኤዶምያስ ።
፲፩ አኮኑ ፡ አንተ ፡ እግዚኦ ፡ ዘገደፍከነ ።
ወኢትወፅእ ፡ አምላክነ ፡ ምስለ ፡ ኃይልነ ።
፲፪ ሀበነ ፡ ረድኤተ ፡ ለምንዳቤነ ።
ወከንቱ ፡ ተአምኖ ፡ በሰብእ ።
፲፫ በእግዚአብሔር ፡ ንገብር ፡ ኃይለ ።
ወውእቱ ፡ ያኅስሮሙ ፡ ለእለ ፡ ይሣቅዩነ ።

መዝሙር ፡ ፻፰ ።
በእንተ መቃብያን ።

፩ እግዚኦ ፡ ኢትጸመመኒ ፡ ስእለትየ ።
፪ እስመ፡አፈ፡ ዐማፂ፡ ወአፈ፡ኃጥእ ፡ አብቀዉ ፡ ላዕሌየ ።
ወነበቡ ፡ ላዕሌየ ፡ በልሳነ ፡ ዐመፃ ።
፫ ዐገቱኒ ፡ ብጽሕአ ። ወጸብኡኒ ፡ በከንቱ ።
፬ ዘእምአፍቀሩኒ ፡ አስተዋደዩኒ ።
ወአንሰ ፡ እጼሊ ።
፭ ፈደዩኒ ፡ እኪተ ፡ ህየንተ ፡ ሠናይት ።
ወጸልኡኒ ፡ ህየንተ ፡ ዘአፍቀርክዎሙ ።
፮ ሢም ፡ ላዕሌሁ ፡ ኃጥአ ።
ወሰይጣን ፡ ይቁም ፡ በየማኑ ።
፯ ወሶበሂ ፡ ይትዋቀሥ ፡ ይፃእ ፡ ተመዊኦ ።
ወጸሎቱኒ ፡ ትኩኖ ፡ ጌጋየ ።
፰ ወይኩና ፡ መዋዕሊሁ ፡ ኅዳጠ ።
ወሢመቶሂ ፡ ይንሣእ ፡ ባዕድ ።
፱ ወይኩኑ ፡ ደቂቁ ፡ ዕጓለ ፡ ማውታ ።
ወብእሲቱኒ ፡ ትኩን ፡ መበለተ ።
፲ ይትሀወኩ ፡ ደቂቁ ፡ ይፍልሱ ፡ ወያስተፍዕሙ ።
ወይስድድዎሙ ፡ እምአብያቲሆሙ ።
፲፩ ወይበርብሮ ፡ በዓለ ፡ ዕዳ ፡ ኵሎ ፡ ንዋዮ ።
ወየሐብልዮ ፡ ነኪር ፡ ኵሎ ፡ ተግባሮ ።
፲፪ ወኢይርከብ ፡ ዘይረድኦ ።
ወኢይምሐርዎሙ ፡ ለዕጓለ ፡ ማውታሁ ።
፲፫ ወይሠረዉ ፡ ደቂቁ ።
በአሐቲ ፡ ትውልድ ፡ ትደምሰስ ፡ ስሙ ።
፲፬ ወትዘከር፡ ኃጢአተ፡ አቡሁ፡በቅድመ፡እግዚአብሔር።
ወኢይደምሰስ ፡ ጌጋየ ፡ ለእሙ ።
፲፭ ወየሀሉ ፡ ቅድመ ፡ እግዚአብሔር ፡ በኵሉ ፡ጊዜ ።
ወይጥፋእ ፡ እምድር ፡ ዝክሩ ።
እስመ ፡ ኢተዘከረ ፡ ይግበር ፡ ምጽዋተ ።
፲፮ ሰደደ ፡ ብእሴ ፡ ነዳየ ፡ ወምስኪነ ።
ጥቡዐ ፡ ልቡ ፡ ለቀቲል ።
፲፯ አብደራ ፡ ለመርገም ፡ ወትምጽኦ ።
አበያ ፡ ለበረከት ፡ ወትርኃቆ ፡ እምኔሁ ።



አቤቱ ፡ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ አመሰግንሃለሁ ፡ ፫
ምሕረትህ ፡ በሰማይ ፡ ላይ ፡ ታላቅ ፡ ናትና ።
እውነትህም ፡ እስከደመናት ፡ ድረስ ፡ ነውና ፡ ፬
በወገኖች ፡ መካከል ፡ እዘምርልሃለሁ ።
አቤቱ ፡ በሰማያት ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ በል ፡ ፭
ክብርህም ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ትሁን ።
ወዳጆችህ ፡ ይድኑ ፡ ዘንድ ፡ ፮
በቀኝህ ፡ አድነኝ ፡ አድምጠኝም ።
እግዚአብሔር ፡ በቅድስናው ፡ ተናገረ ፡ ፯
ደስ ፡ ይለኛል ፤ ሴኬምንም ፡ እካፈላለሁ ፤
የሱኮትንም ፡ ሸለቆ ፡ እሰፍራለሁ ።
ገለዓድ ፡ የእኔ ፡ ነው ፡ ምናሴም ፡ የእኔ ፡ ነው ፡ ፰
ኤፍሬም ፡ የራሴ ፡ መጠጊያ ፡ ነው ፤
ይሁዳ ፡ ንጉሤ ፡ ነው ፤
ሞአብ ፡ መታጠቢያዬ ፡ ነው ። ፱
በኤዶምያስ ፡ ላይም ፡ ጫማዬን፡ እዘረጋለሁ ።
ፍልስጥኤም ፡ ይገዛልኛል ።
ወደ ፡ ጽኑ፡ አገር ፡ ማን ፡ ይወስደኛል ? ፲
ማንስ ፡ ወደ ፡ ኤዶምያስ ፡ ይመራኛል ?
አቤቱ ፡ የጣልኸን ፡ አንተ ፡ አይደለህምን ? ፲፩
አምላክ ፡ ሆይ፡ ከሠራዊታችን፡ ጋራ ፡ አትወጣም ።
በመከራችን ፡ ጊዜ ፡ ረድኤትን ፡ ስጠን ፡ ፲፪
የሰውም ፡ ማዳን ፡ ከንቱ ፡ ነው ።
በእግዚአብሔር ፡ ኃይልን ፡ እናደርጋለን ፡ ፲፫
እርሱም ፡ የሚያስጨንቁንን ፡ ያዋርዳል ።

መዝሙር ፡ ፻፰ ።
ስለ ፡ መቃብያን ።

አምላክ ፡ ሆይ ፡ ምስጋናዬን ፡ ዝም ፡ አትበል ፤ ፩
የኃጢአተኛ አፍና የተንኰለኛ አፍ በላዬ ተላቅቀውብኛልና ። ፪
በሽንገላ ፡ አንደበትም ፡ በላዬ ፡ ተናገሩ ።
በጥል ፡ ነገር ፡ ከበቡኝ ፡ በከንቱም ፡ ተሰለፉብኝ ፡ ፫
ስለወደድኋቸው፡ ፋንታ፡ አጣሉኝ፡ እኔ፡ ግን፡ እጸልያለሁ። ፬
በመልካም ፡ ፋንታ ፡ ክፉን ፡ ፭
ስለ፡ወደድኋቸውም ፡ ጠላትንትን ፡ መለሱልኝ ።
በላዩ ፡ ኀጢአተኛን ፡ ሹም ፡ ፮
ሰይጣንም ፡ በቀኙ ፡ ይቁም ።
በተሟገተም ፡ ጊዜ ፡ ተረትቶ ፡ ይውጣ ፡ ፯
ጸሎቱም ፡ ኀጢአት ፡ ትሁንበት ።
ዕድሜዎቹም ፡ ጥቂት ፡ ይሁኑ ፡ ፰
ሹመቱንም ፡ ሌላ ፡ ይውሰድ ።
ልጆቹም ፡ ድኃ ፡ አደግ ፡ ይሁኑ ፡ ፱
ሚስቱም ፡ መበለት ፡ ትሁን ።
ልጆቹም ፡ እየተቅበዘበዙ ፡ ይዙሩ፡ይለምኑም ፡ ፲
ከስፍራቸውም ፡ ይባረሩ ።
ባለዕዳም ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡ ይበርብረው ፡ ፲፩
የደከመበትን ፡ ሁሉ ፡ ሌሎች ፡ ይንጠቁት ።
የሚያግዘውም ፡ አያግኝ ፡ ፲፪
ለድሀ ፡ አደግ ፡ ልጆቹም ፡ የሚራራ ፡ አይኑር ።
ልጆቹ ፡ ይጥፉ ፡ ፲፫
በአንድ ፡ ትውልድ ፡ ስሙ ፡ ይደምሰስ ።
የአባቶቹ፡ኀጢአት፡በእግዚአብሔር፡ ፊት፡ ትታሰብ፡ ፲፬
የእናቱም ፡ ኀጢአት ፡ አትደምሰስ ።
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ሁልጊዜ ፡ ይኑሩ ፡ ፲፭
ምሕረትን ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ አላሰበምና ፡
መታሰቢያቸው ፡ ከምድር ፡ ይጥፋ ።
ችጋረኛንና ፡ ምስኪንን ፡ ፲፮
ልቡ ፡ ተሰበረውንም ፡ ሰው ፡ ይገድል ፡ ዘንድ፡ አሳደደ ።
መርገምን ፡ ወደደ ፡ ወደ ፡ እርሱም ፡ መጣች ፡ ፲፯
በረከትንም ፡ አልመረጠም ፡ ከእርሱም ፡ራቀች ።

፲፰ ወለብሳ ፡ ለመርገም ፡ ከመ ፡ ልብስ ።
ወቦአ ፡ ከመ ፡ ማይ ፡ ውስተ ፡ አማዑቱ ።
ወከመ ፡ ቅብዕ ፡ ውስተ ፡ አዕፅምቲሁ ።
፲፱ ለትኩኖ ፡ ከመ ፡ ልብስ ፡ ዘይትዐጸፍ ።
ወከመ ፡ ቅናት ፡ ዘይቀንት ፡ ዘልፈ ።
፳ ዝግብር ፡ ለእለ ፡ ያስተዋድዩኒ ፡ ኀበ ፡
ወለእለ ፡ ይነቡ ፡ እኩየ ፡ ላዕለ ፡ ነፍስየ ።
፳፩ አንተሰ ፡ እግዚኦ ፡ እግዚእየ ፡ ግበር ፡ ሣህለከ ፡
ላዕሌየ ፡ በእንተ ፡ ስምከ ።
እስመ ፡ ሠናይ ፡ ምሕረትከ ።
፳፪ አድኅነኒ ፡ እስመ ፡ ነዳይ ፡ ወምስኪን ፡ አነ ።
ልብየኒ ፡ ደንገጸኒ ፡ በውስጥየ ።
፳፫ ወኀለቁ ፡ ከመ ፡ ጽላሎት ፡ ዘኀለፈ ።
ወተነገፍኩ ፡ ከመ ፡ አንበጣ ።
፳፬ ወደከመኒ ፡ ብረክየ ፡ በጾም ።
ወሥሕከ ፡ ሥጋየ ፡ በኀጢአ ፡ ቅብዕ ።
፳፭ ወአንሰ ፡ ተጽዕልኩ ፡ በኀቤሆሙ ።
ሶበ ፡ ይሬእዩኒ ፡ የሐውሱ ፡ ርእሶሙ ።
፳፮ ርድአኒ ፡ እግዚኦ ፡ አምላኪየ ።
ወአድኅነኒ ፡ በእንተ ፡ ምሕረትከ ።
፳፯ ወያእምሩ ፡ ከመ ፡ እዴከ ፡ ይእቲ ፡ ዛቲ ።
አንተሰ ፡ እግዚኦ ፡ ገበርከ ።
፳፰ እሙንቱሰ ፡ ይረግሙ ፡ ወአንተ ፡ ባርክ ።
ይትኀፈሩ ፡ እለ ፡ ይትነሥኡ ፡ ላዕሌየ ።
ወገብርከሰ ፡ ይትፌሣሕ ።
፳፱ ይልበሱ ፡ ኀፍረተ ፡ ወኀሳረ ፡ እለ ፡ ያስተዋድዩኒ ።
ወይትዐጸፍዋ ፡ ከመ ፡ ዐጽፍ ፡ ለኀጢአቶሙ ።
፴ እገኒ ፡ በአፉየ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ፈድፋደ ።
ወእሴብሖ ፡ በማዕከለ ፡ ብዙኃ ።
እስመ ፡ ቆመ ፡ በየማነ ፡ ነዳይ ።
፴፩ ከመ ፡ ያድኅና ፡ ለነፍስየ ፡ እምእለ ፡ ሮድዋ ።

መዝሙር ፡ ፻፱ ።

ትንቢት በእንተክርስቶስ ።

፩ ይቤሎ ፡ እግዚእ ፡ ለእግዚእየ ፡ ንበር ፡ በየማንየ ።
እስከ፡ ገብአሙ፡ ለጸላእትከ፡ ታሕተ፡መከየደ፡እገሪከ።
፪ በትረ ፡ ኀይል፡ይፌኑ፡ለከ፡እግዚአብሔር ፡ እምጽዮን።
ወትኬንን ፡ በማእከለ ፡ ጸላእትከ ።
፫ ምስሌከ ፡ ቀዳማዊ ፡ በዕለተ ፡ ኃይል ።
በብርሃኖሙ ፡ ለቅዱሳን ።
ወለድኩከ ፡ እምከርሥ ፡ እምቅድመ ፡ ኮከበ ፡ ጽባሕ ።
መሐለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወኢይኔስሕ ።
፬ አንተ፡ካህኑ፡ለዓለም፡በከመ፡ሢመቱ፡ለመልከ፡ጼዴቅ።
፭ እግዚአብሔር ፡ በየማንከ ።
ይቀጠቅጦሙ ፡ ለነገሥት ፡ በዕለተ ፡ መዓቱ ።
፮ ወይኬንኖሙ ፡ ለአሕዛብ ፡ ወያበዝኃ ፡ አብድንተ ።
ወይሰብር ፡ አርእስተ ፡ ብዙኃን ፡ በዲበ ፡ ምድር ።
፯ እምውኂዝ ፡ ስትዩ ፡ ማየ ፡ በፍኖት ።
ወበእንተዝ ፡ ይትሌዐል ፡ ርእስ ።

መዝሙር ፡ ፻፲ ።

በእንተ ትፋሥሕ ወበእንተ ሕዝቅያስ ።

፩ እገኒ ፡ ለከ ፡ እግዚኦ ፡ በኵሉ ፡ ልብየ ።
፪ በምክረ ፡ ራትዓን ፡ ወበማኅበር ፡ ዐቢይ ፡ ግብረ ፡
እግዚአብሔር ።
ወትትሐወሥ ፡ ውስተ ፡ ኵሉ ፡ ፈቃዱ ።



መርገምን ፡ እንደ ፡ ልብስ ፡ ለበሳት ፡ ፲፰
እንደ ፡ ውኃም ፡ ወደ ፡ አንጀቱ ፡
እንደ ፡ ቅቤም ፡ ወደ ፡ አጥንቱ ፡ ገባች ።
እንደ ፡ ልብስ ፡ የሚለበስ ፡ ፲፱
እንደ ፡ ትጥቅም ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ የሚቀነት ፡ ይሁነው ።
ይህ ፡ ሥራ ፡ ከእግዚአብሔር ዘንድ ፡ በሚያጣሉኝ ፡ ፳
በነፍሴም ፡ ላይ ፡ ክፉን ፡ በሚናገሩ ፡ ነው ።
አንተ ፡ ግን ፡ አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ስለ፡ ስምህ፡ምሕረትህን ፡ ፳፩
በእኔ ፡ ላይ ፡ አድርግ ፡
ምሕረትህ ፡ መልካም ፡ ናትና ፡ አድነኝ ።
እኔ ፡ ችግረኛ ፡ ምስኪንም ፡ ነኝ ፡
ልቢም ፡ በውስጤ ፡ ደነገጠብኝ ። ፳፪
እንደ ፡ አለፈ ፡ ጥላ ፡ አለቅሁ ።
እንደ ፡ አንበጣም ፡ ረገፍሁ ። ፳፫
ጉልበቶቼ ፡ በጾም ፡ ደከሙ ፡ ፳፬
ሥጋዬም ፡ ቅቤ ፡ በማጣት ፡ ከሳ ።
እኔም ፡ በእነርሱ ፡ ዘንድ ፡ ለነውር ፡ ሆንሁ ፡ ፳፭
ባዩኝ ፡ ጊዜ ፡ ራሳቸውን ፡ ነቀነቁ ።
አቤቱ ፡ አምላኬ ፡ እርዳኝ ፡ ፳፮
እንደ ፡ ምሕረትህም ፡ አድነኝ ።
አቤቱ ፡ እጅህ ፡ ይህች ፡ እንደሆነች ፡ ፳፯
አንተም ፡ ይህችን ፡ እንደ ፡ አደረግህ ፡ ይወቁ
እነርሱ ፡ ይራገማሉ ፡ አንተ ፡ ግን ፡ መርቅ ፡ ፳፰
በእኔ ፡ ላይ ፡ የሚነሡ ፡ ይፈሩ ፡
ባሪያህ ፡ ግን ፡ ደስ ፡ ይበለው ።
የሚያጣሉኝ ፡ ኀፍረትን ፡ ይልበሱ ፡ ፳፱
ኀፍረታቸውን ፡ እንደ ፡ መጐናጸፊያ ፡ ይልበሷት ።
እግዚአብሔርን ፡ በአፌ ፡ እጅግ ፡ አመሰግነዋለሁ ፡ ፴
በብዙዎችም ፡ መካከል ፡ አከብረዋለሁ ፡
ነፍሴን ፡ ከሚያሳድዷት ፡ ያድን ፡ ዘንድ ፡ ፴፩
በድሀ ፡ ቀኝ ፡ ቆሟልና ።

መዝሙር ፡ ፻፱ ።

ትንቢት ፡

ጌታ ፡ ጌታዬን ፡ ጠላቶችህን ፡ ለእግርህ ፡ መረገጫ ፡ ፩
እስካደርግልህ ፡ በቀኜ ፡ ተቀመጥ ፡ አለው ።
እግዚአብሔር ፡ የኃይልን ፡ በትር ፡ ከጽዮን ፡ ይልክልሃል ፡ ፪
በጠላቶችህም ፡ መካከል ፡ ግዛ ።
ከአንተ ፡ ጋራ ፡ ቀድሞ ፡ በኃይልህ ፡ ቀን ፡ በቅዱሳን ፡ ብርሃን ፫
ከአጥቢያ ፡ ኮከብ ፡ አስቀድሞ ፡ ከሆድ ፡ ወለድሁህ ።
እንደ ፡ መልከ ፡ ጼዴቅ ፡ ሥርዓት ፡ ፬
አንተ ፡ ለዘላለም ፡ ካህን ፡ ነህ ፡ ብሎ ።
እግዚአብሔር ፡ ማለ ፡ አይጸጸትም ።
እግዚአብሔር ፡ በቀኝህ ፡ ፭
ነገሥታትን ፡ በቍጣው ፡ ቀን ፡ ይቀጠቅጣቸዋል ።
በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ ይፈርዳል ፡ ፮
ሬሳዎችንም ፡ ያበዛል ።
በሰፊ ፡ ምድር ፡ ላይ ፡ ራሶችን፡ ይቀጠቅጣል ።
በመንገድ ፡ ከፈሳሽ ፡ ውሀ ፡ ይጠጣል ፡ ፯
ስለዚህ ፡ ራስ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ።

መዝሙር ፡ ፻፲ ።

ስለ ትፋሥሕ ፡ ስለ ሕዝቅያስ ።

ሃሌ ፡ ሉያ ፡

አቤቱ ፡ በቅኖች ፡ ሸንጎ ፡ በጉባኤም ፡ ፩
በፍጹም ፡ ልቤ ፡ አመሰግንሃለሁ ።
የእግዚአብሔር ፡ ሥራ ፡ ታላቅ ፡ ናት ፡ ፪
ለሚሿትም ፡ ሁሉ ፡ ያማረች ፡ ናት ።

፫ አሚን ፡ ወዕበየ ፡ ስብሐት ፡ ምግባሩ ።
ወጽድቁኒ ፡ ይነብር ፡ ለዓለም ።
፬ ተዝካረ ፡ ገብረ ፡ ለስብሐቲሁ ።
መሐሪ ፡ ወመስተሣህል ፡ እግዚአብሔር ።
፭ ወወሀቦሙ ፡ሲሳዮሙ ፡ ለእለ ፡ ይፈርህዎ ።
ወተዘከረ ፡ ኪዳኖ ፡ ዘለዓለም ።
ወአርአዮሙ ፡ ለሕዝቡ ፡ ኃይለ ፡ ምግባሩ ።
፮ ከመ ፡ የሀቦሙ ፡ ርስተ ፡ ዘአሕዛብ ።
፯ ግብረ ፡ እደዊሁ ፡ ጽድቅ ፡ ወርትዕ ።
፰ ወእሙን ፡ ኵሉ ፡ ትእዛዙ ። ወጽኑዕ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ።
ወግቡር ፡ በጽድቅ ፡ ወበርትዕ ።
፱ መድኃኒተ ፡ ፈነወ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሕዝቡ ።
ወአዘዘ ፡ ሥርዓቶ ፡ ዘለዓለም ።
ቅዱስ ፡ ወግሩም ፡ ስመ ፡ ዚአሁ ።
፲ ቀዳሚሃ ፡ ለጥበብ ፡ ፈሪሀ ፡ እግዚአብሔር ።
ምክር ፡ ሠናይት ፡ ለኵሉ ፡ ዘይገብራ ።
ወስብሐቲሁኒ ፡ ይነብር ፡ ለዓለም ።

መዝሙር ፡ ፻፲፩ ።

በእንተ ሕዝቅያስ ።

፩ ብፁዕ ፡ ብእሲ ፡ ዘይፈርሆ ፡ለእግዚአብሔር ።
ወዘይፈቅድ ፡ ትእዛዞ ፡ ፈድፋደ ።
፪ ወይከውን ፡ ጽኑዐ ፡ ዘርዐ ፡ ውስተ ፡ ምድር ።
ትውልደ ፡ ጻድቃን ፡ ይትባረኩ ።
፫ ክብር ፡ ወብዕል ፡ ውስተ ፡ ቤቱ ።
ወጽድቁኒ ፡ ይነብር ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ።
፬ ሠረቀ ፡ ብርሃን ፡ ለራትዓን ፡ በውስተ ፡ ጽልመት ።
፭ መሐሪ ፡ ወመስተሣህል ፡ እግዚአብሔር ፡ ወጻድቅ ፡
እምላክነ ።
ብእሲ ፡ መሐሪ ፡ ወመስተሣህል ፡ ወኄር ።
፮ ወይኤቅም ቃሎ በውስተ ፍትሕ ። ወኢይትሀወክ ለዓለም ።
ዝክረ ፡ ጻድቅ ፡ ለዓለም ፡ ይሄሉ ።
፯ ወኢይፈርሕ ፡ እምነገር ፡ እኩይ ።
ጥቡዕ ፡ ልቡ ፡ ለተወክሎ ፡ በእግዚአብሔር ።
፰ ጽኑዕ ፡ ልቡ ፡ ወኢይትሀወክ ፡ ለዓለም ።
እስከ ፡ ይሬኢ ፡ በጸላእቱ ።
፱ ዘረወ ፡ ወወሀበ ፡ ለነዳይ ።
ወጽድቁኒ ፡ ይነብር ፡ ለዓለም ።
ወይትሌዐል ፡ ቀርኑ ፡ በክብር ።
፲ ይሬኢ ፡ ኃጥእ ፡ ወይትመዓዕ ።
ወየሐቂ ፡ ስነኒሁ ፡ ወይትመሰው ።
ወተሐልቅ ፡ ፍትወቶሙ ፡ ለኃጥአን ።

መዝሙር ፡ ፻፲፪ ።

በእንተ ትሩፋን ።

፩ ሰብሕዎ ፡ አግብርቲሁ ፡ ለእግዚአብሔር ።
ወሰብሑ ፡ ለስመ ፡ እግዚአብሔር ።
ወይኩን ቡሩክ ፡ ስሙ ፡ ለእግዚአብሔር ።
፪ እምይእዜ ፡ ወእስከ ፡ ለዓለም ።
፫ እምሥራቀ ፡ ፀሐይ ፡ እስከነ ፡ ዐረብ ።
ይትአኰት ፡ ስሙ ፡ ለእግዚአብሔር ።
፬ ልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡መልዕልተ ፡ ኵሉ ፡ አሕዛብ ።
ወውስተ ፡ ሰማያት ፡ ስብሐቲሁ ።
፭ መኑ ፡ ከመ ፡ እግዚአብሔር ፡አምላክነ ።
ዘይነብር ፡ ውስተ ፡ አርያም ፡ ወይሬኢ ፡ ዘበታሕቱ ።



ሥራውም ፡ በክብርና ፡ በጌጥ ፡ ነው ፤ ፫
ጽድቁም ፡ ለዘላለም ፡ ይኖራል ።
ለተአምራቱ ፡ መታሰቢያን ፡ አደረገ ፤ ፬
እግዚአብሔር ፡ መሐሪና፡ ይቅር ፡ ባይ ፡ ነው ።
ለሚፈሩት ፡ ምግብን ፡ ሰጣቸው ፤ ፭
ኪዳኑንም ፡ ለዘላለም ፡ ያስባል ።
የአሕዛብን ፡ ርስት ፡ ይሰጣቸው ፡ ዘንድ ፤ ፮
ለሕዝቡ ፡ የሥራውን ፡ ብርታት ፡ አሳየ ።
የእጆቹ ፡ ሥራ ፡ እውነተኛ ፡ ፍርድ ፡ ነው ፤ ፯
ትእዛዙም ፡ ሁሉ ፡ የታመነ ፡ ነው ።
ለዘላለምም ፡ የጸና ፡ ነው ፤ ፰
በእውነትና ፡ በቅንም ፡ የተሠራ ፡ ነው ።
መድኃኒትንም ፡ ለሕዝቡ ፡ ሰደደ ፤ ፱
ኪዳኑንም ፡ ለዘላለም ፡ አዘዘ ።
ስሙ ፡ የተቀደሰና ፡ የተፈራ ፡ ነው ።
የጥበብ ፡ መጀመሪያ ፡እግዚአብሔርን መፍራት ፡ ነው ፤ ፲
ለሚያደርጓትም ፡ ሁሉ ፡ በጎ ፡ ማስተዋል ፡ አላቸው ።
ምስጋናውም ፡ ለዘላለም ፡ ይኖራል ።

መዝሙር ፡ ፻፲፩ ።

ስለ ሕዝቅያስ ።

ሃሌ ፡ ሉያ ፤
እግዚአብሔርን ፡ የሚፈራ ፤ ፩
ትእዛዙንም ፡ ፈጽሞ፡ የሚጠብቅ ፡ ሰው ፡ ምስጉን ፡ ነው ።
ዘሩ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ብርቱ ፡ ይሆናል ፤ ፪
የቅኖች ፡ ትውልድ ፡ ትባረካለች ።
ክብርና ፡ ባለጠግነት ፡ በቤቱ ፡ ነው ፤ ፫
ጽድቁም ፡ ለዘላለም ፡ ይኖራል ።

ለቅኖች ፡ ብርሃን ፡ በጨለማ ፡ ወጣ ፤ ፬
መሐሪና ፡ ይቅር ፡ ባይ ፡ ጻድቅም ፡ ነው ።
ቸር ፡ ሰው ፡ ይራራል ፡ ያበድራልም ፤ ፭
በፍርድም ፡ ነገሩን ፡ ይፈጽማል ።
ለዘላለም ፡ አይናወጥም ፤ ፮
የጻድቅ ፡ መታሰቢያ ፡ ለዘላለም ፡ ይኖራል ።
ከክፉ ፡ ነገር ፡ አይፈራም ፤ ፯
በእግዚአብሔር ፡ ለመታመን ፡ ልቡ ፡ የጸና ፡ ነው ።
ሞኞቹን ፡ በጠላቶቹ ፡ ላይ ፡ እስኪያይ ፡ ድረስ ፤ ፰
ልቡ ፡ ጽኑ ፡ ነው ፡ አይፈራም ።
ለገስ ፡ ለችጋረኞችም ሰጠ ፤ ፱
ጽድቁ ፡ ለዘላለም ፡ ይኖራል ።
ሥልጣኑ ፡ በክብር ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ።
ኀጢአተኛም ፡ አይቶ ፡ ይቆጣል ፤ ፲
ጥርሱንም ፡ ያፏጫል ፡ ይቀልጣልም ፤
የኀጢአተኞችም ፡ ምኞት ፡ ትጠፋለች ።

መዝሙር ፡ ፻፲፪ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

ሃሌ ፡ ሉያ ፡ ፩
የእግዚአብሔር ፡ ባሪያዎች ፡ ሆይ ፡ አመስግኑት ፤
የእግዚአብሔርንም ፡ ስም ፡ አመስግኑ ።
ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ድረስ ፤ ፪
የእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ቡሩክ ፡ ይሁን ።
ከፀሐይ ፡ መውጫ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ መግቢያው ፡ ድረስ ፤ ፫
የእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ይመስገን ።
እግዚአብሔር፡ በአሕዛብ፡ ሁሉ ፡ ላይ፡ ከፍተኛ ፡ ነው ። ፬
ክብሩም ፡ ከሰማያት ፡ በላይ ፡ ነው ።
እንደ ፡ አምላካችን ፡ እንደ ፡እግዚአብሔር ፡ ማን፡ አለ ? ፭
በላይ ፡ የሚኖር ።

፮ በሰማይኒ ፡ ወበምድርኒ ።
፯ ዘያነሥኦ ፡ እምድር ፡ ለነዳይ ።
ወያሌዕሎ ፡ እመሬት ፡ ለምስኪን ።
፰ ከመ ፡ ያንብሮ ፡ ምስለ ፡ መላእክቲሁ ።
ወምስለ ፡ መላእክተ ፡ ሕዝቡ ።
፱ ዘያነብራ ፡ ለመካን ፡ ውስተ ፡ ቤቱ ።
ወያስተፌሥሓ ፡ ለእመ ፡ ውሉድ ።

መዝሙር ፡ ፻፲፫ ።

በእንተ ትሩፋን ።

፩ አመ ፡ ይወጽኡ ፡ እስራኤል ፡ እምግብፅ ።
ወቤተ ፡ ያዕቆብ ፡ እምሕዝበ ፡ ፀር ።
፪ ወኮነ ፡ ይሁዳ ፡ መቅደሶ ። ወእስራኤልኒ ፡ ምኵናኖ ።
፫ ባሕርኒ ፡ ርእየት ፡ ወጐየት ።
ወዮርዳኖስኒ ፡ ገብአ ፡ ድኅሬሁ ።
፬ አድባር ፡ አንፈርዐፁ ፡ ከመ ፡ ሐራጊት ።
ወአውግርኒ ፡ ከመ ፡ መሓስዕ ፡ አባግዕ ።
፭ ምንተ ፡ ኮንኪ ፡ ባሕር ፡ ዘጐየይኪ ።
ወአንተኒ ፡ ዮርዳኖስ ፡ ዘገባእከ ፡ ድኅሬከ ።
፮ አድባር ፡ ዘአንፈርዐፅክሙ ፡ ከመ ፡ ሐራጊት ።
ወአውግርኒ ፡ ከመ ፡ መሓስዕ ፡ አባግዕ ።
እምቅድመ፡ገጹ፡ለእግዚአብሔር ፡አድለቅለቀት፡ምድር ።
፯ እምቅድመ ፡ ገጹ ፡ ለአምላከ ፡ ያዕቆብ ።
፰ ዘይሬስያ ፡ ለኰኵሕ ፡ አንቅዕተ ፡ ማያት ።
ወለእዝኅ ፡ በዐዘቅተ ፡ ማያት ።
፱ አኮ ፡ ለነ ፡ እግዚኦ ፡ አኮ ፡ ለነ ።
ለስመ ፡ ዚአከ ፡ ሀብ ፡ ስብሐተ ።
በምሕረትከ ፡ ወበጽድቅከ ።
፲ ከመ ፡ ኢይበሉነ ፡ አሕዛብ ፡ አይቴ ፡ ውእቱ ፡
አምላኮሙ ።

፲፩ አምላክነሰ ፡ ውስተ ፡ ሰማይ ፡ ላዕለ ።
በሰማይኒ ፡ ወበምድርኒ ።
ኵሎ ፡ ዘፈቀደ ፡ ገብረ ፡ እግዚአብሔር ።
፲፪ አማልክቲሆሙ ፡ ለአሕዛብ ፡ ዘወርቅ ፡ ወዘብሩር ።
ግብረ ፡ እደ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ።
፲፫ አፍ ፡ ቦሙ ፡ ወኢይነቡ ።
ዐይን ፡ ቦሙ ፡ ወኢይሬእዩ ።
፲፬ እዝን ፡ ቦሙ ፡ ወኢይሰምዑ ።
አንፍ ፡ ቦሙ ፡ ወኢያጼንዉ ።
፲፭ እድ ፡ ቦሙ ፡ ወኢይገሡ ።
እግር ፡ ቦሙ ፡ ወኢየሐውሩ ።
ወኢይነቡ ፡ በጐራዒቶሙ ።
ወአልቦ ፡ መንፈስ ፡ ውስተ ፡ አፉሆሙ ።
፲፮ ከማሆሙ ፡ ለይኩኑ ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ ገብርዎሙ ።
ወኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይትዌከሉ ፡ ቦሙ ።
፲፯ ቤተ ፡ እስራኤል ፡ ተወከሉ ፡ በእግዚአብሔር ።
ረዳኢሆሙ ፡ ውእቱ ፡ ወምእመኖሙ ።
፲፰ ቤተ ፡ አሮን ፡ ተወከሉ ፡ በእግዚአብሔር ።
ረዳኢሆሙ ፡ ውእቱ ፡ ወምእመኖሙ ።
፲፱ እለ ፡ ትፈርህዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ተወከሉ ፡
በእግዚአብሔር ።
ረዳኢሆሙ ፡ ውእቱ ፡ ወምእመኖሙ ።
፳ እግዚአብሔር ፡ ተዘከረነ ፡ ወባረከነ ።
ባርከ ፡ ቤተ ፡ እስራኤል ። ወባርከ ፡ ቤተ ፡ አሮን ።
፳፩ ባርኮሙ፡ለኵሎሙ፡ እለ፡ይፈርህዎ ፡ለእግዚአብሔር ።
ለንኡሶሙ ፡ ወለዐቢዮሙ ።
፳፪ ይዌስክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ላዕሌክሙ ።
ላዕሌክሙ ፡ ወላዕለ ፡ ውሉድክሙ ።



በሰማይና ፡ በምድር ፡ የተዋረዱትን ፡ የሚያይ ፡ ፮
ከአለቶችና ፡ ከሕዝቡም ፡ አለቆች ፡ ጋራ ፡ ያኖረው ፡ ዘንድ ። ፯
ችጋረኛን ፡ ከመሬት ፡ የሚያነሣ ፡ ፰
ምስኪኑንም ፡ ከትቢያ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ የሚያደርግ ።
መካኒቱን ፡ በቤት ፡ የሚያኖራት ፡ ፱
ደስ ፡ የተሰኘችም ፡ የልጆች ፡ እናት ፡ የሚያደርጋት ።

መዝሙር ፡ ፻፲፫ ።

ስለትሩፋን ።

ሃሌ ፡ ሉያ ፡
እስራኤል ፡ ከግብፅ ፡ ፩
የያዕቆብም ፡ ቤት ፡ ከእንግዳ ፡ ሕዝብ ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ።
ይሁዳ ፡ መቅደሱ ፡ ፪
እስራኤልም ፡ ግዛቱ ፡ ሆነ ።
ባሕር ፡ አየች ፡ ሸሸችም ፡ ፫
ዮርዳኖስም ፡ ወደ ፡ ኋላው ፡ ተመለሰ ።
ተራሮች ፡ እንደ ፡ ኮርማዎች ፡ ፬
ኮረብቶችም ፡ እንደ ፡ ጠቦቶች ፡ ዘለሉ ።
አንቺ ፡ ባሕር ፡ የሸሸሽ ፡ ፭
አንቺም ፡ ዮርዳኖስ ፡ ወደ ፡ ኋላሽ ፡ ያፈገፈግሽ ፡ ምን ፡ ሆናችኋል ።
እናንተም ፡ ተራሮች ፡ እንደ ፡ ኮርማዎች ፡ ፮
ኮረብቶችስ ፡ እንደ ፡ ጠቦቶች ፡ ለምን ፡ ዘለላችሁ ?
ድንጋዩን ፡ ወደ ፡ ውኃ ፡ መቆሚያ ፡ ፯
ጭንጫውንም ፡ ወደ ፡ ውኃ ፡ ምንጭ ፡ ከለወጠ ፡
ከያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ ፊት ፡ ፰
ከጌታ ፡ ፊት ፡ ምድር ፡ ተናወጠች ።
ለእኛ ፡ አይደለም ፡ አቤቱ ፡ ለእኛ ፡ አይደለም ፡ ፱
ነገር ፡ ግን ፡ ለስምህ ፡
ስለ ፡ ምሕረትህ ፡ ስለ ፡ እውነትህም ፡ ምስጋናን ፡ ስጥ ።
አሕዛብ ፡ አምላካቸው ፡ ወዴት ፡ ነው ፡ አይበሉ ። ፲

አምላካችንስ ፡ በላይ ፡ በሰማይ ፡ ነው ፡ ፲፩
በሰማይም ፡ በምድርም ፡
የፈቀደውን ፡ ሁሉ ፡ ያደጋርል ።
የአሕዛብ ፡ ጣዖታቶች ፡ የወርቅና ፡ የብር ፡ ፲፪
የሰውም ፡ እጅ ፡ ሥራ ፡ ናቸው ።
አፍ ፡ አላቸው ፡ አይናገሩም ፡ ፲፫
ዓይን ፡ አላቸው ፡ አያዩምም ።
ጆሮ ፡ አላቸው ፡ አይሰሙምም ፡ ፲፬
አፍንጫ ፡ አላቸው ፡ አያሸቱምም ።
እጅ ፡ አላቸው ፡ አይዳስሱምም ፡ ፲፭
እግር ፡ አላቸው ፡ አይሄዱምም ፤
በጉረሮቸውም ፡ አይናገሩም ።
የሠሪቻቸውም ፡ ፲፮
የሚያምኑባቸውም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ እነርሱ ፡ ይሁኑ ።
የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ታመኑ ፤ ፲፯
ረድኤታቸውና ፡ መታመኛቸው ፡ እርሱ ፡ ነው ።
የአሮን ፡ ቤት ፡ ሆይ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ታመኑ ፡ ፲፰
ረድኤታቸውና ፡ መታመኛቸው ፡ እርሱ ፡ ነው ።
እግዚአብሔርን ፡ የምትፈሩ ፡ ሆይ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ታመኑ ፲፱
ረድኤታቸውና ፡ መታመኛቸው ፡ እርሱ ፡ ነው ።
እግዚአብሔር ፡ አሰበን ፤ ይባርከንማል ፡ ፳
የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ይባርካል ።
የአሮንንም ፡ ቤት ፡ ይባርካል ፡
እግዚአብሔር ፡ የሚፈሩትን ፡ ፳፩
ትንንሾችንና ፡ ትልልቆችን ፡ ይባርካል ።
እግዚአብሔር በናንተ ፡ ላይ ፡ ፳፪
በላያችሁና ፡ በልጆቻችሁም ፡ ላይ ፡ ይደር ።

፳፫ ቡሩካኑ ፡ አንትሙ ፡ ለእግዚአብሔር ።
ዘገብረ ፡ ሰማየ ፡ ወምድረ ።
፳፬ ሰማየ ፡ ሰማያት ፡ ለእግዚአብሔር ።
ምድረሰ ፡ ወሀበ ፡ ለዕጓለ ፡ እመሕያው ።
፳፭ ዘአኮ ፡ ሙታን ፡ ይሴብሑከ ፡ እግዚኦ ።
ወኢኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይወርዱ ፡ ውስተ ፡ ሲኦል ።
፳፮ ንሕነ ፡ ሕያዋን ፡ ንባርክ ፡ ለእግዚአብሔር ።
እምይእዜ ፡ ወእስከ ፡ ለዓለም ።

መዝሙር ፡ ፻፲፬ ።

በእንተ ሕዝቅያስ ።

፩ አፍቀርኩ፡እስመ፡ሰምዓኒ፡ እግዚአብሔር ቃለ፡ስእለትየ።
፪ ወአጽምዐ ፡ እዝኖ ፡ ኀቤየ ።
ወጸዋዕክዎ ፡ በመዋዕልየ ።
፫ አኀዘኒ ፡ ፃዕረ ፡ ሞት ።
ወረከበኒ ፡ ሕማመ ፡ ሲኦል ።
ሕማም ፡ ወምንዳቤ ፡ ረከበኒ ።
፬ ጸዋዕኩ ፡ ስመ ፡ እግዚአብሔር ።
እግዚኦ ፡ ባልሓ ፡ ለነፍስየ ።
፭ መሐሪ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወጻድቅ ።
ወአምላክነሂ ፡ መስተሣህል ።
፮ የዐቅብ ፡ ሕፃናተ ፡ እግዚአብሔር ።
ተመንደብኩሂ ፡ ወአድኀነኒ ።
፯ ግብኢ ፡ ነፍስየ ፡ ውስተ ፡ ዕረፍትኪ ።
እስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ረዳኢኪ ።
፰ እስመ ፡ አድኃና ፡ ለነፍስየ ፡ እሞት ።
ወለአዕይንትየኒ ፡ እምአንብዕ ።
ወለእገርየኒ ፡ እምዳኅፅ ።
፱ ከመ ፡ አሥምሮ ፡ ለእግዚአብሔር በብሔረ ፡ ሕያዋን ።

መዝሙር ፡ ፻፲፭ ።

በእንተ ሕዝቅያ ።

፩ አመንኩ ፡ በዘነበብኩ ።
ወአንሰ ፡ ብዙኀ ፡ ሐመምኩ ።
፪ አንሰ ፡ እቤ ፡ እምግዕዝየ ፡ ኵሉ ፡ ሰብእ ፡ ሐሳዊ ፡ ውእቱ ።
፫ ምንተኑ ፡ አዐስዮ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በእንተ ፡ ኵሉ ፡
ዘገብረ ፡ ሊተ ።
፬ ጽዋዐ ፡ ሕይወት ፡ እትሜጦ ።
ወስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ እጼውዕ ።
፭ ወእሁብ ፡ ብፅዐትየ ፡ ለእግዚአብሔር ።
በቅድመ ፡ ኵሉ ፡ ሕዝብ ።
፮ ክቡር ፡ ሞቱ ፡ ለጻድቅ ፡ በቅድመ ፡ እግዚአብሔር ።
፯ እግዚኦ ፡ አነ ፡ ገብርከ ። ገብርከ ፡ ወልደ ፡ አመትከ ።
ወሰበርከ ፡ መዋቅሕትየ ።
፰ ለከ ፡ እሠውዕ ፡ መሥዋዕተ ፡ ስብሐት ።
፱ ወእሁብ ፡ ብፅዐትየ ፡ ለእግዚአብሔር ።
በቅድመ ፡ ኵሉ ፡ ሕዝብ ።
፲ ለዐጸደ ፡ ቤተ ፡ እግዚአብሔር ።
ወበማእከሌኪ ፡ ኢየሩሳሌም ።

መዝሙር ፡ ፻፲፮ ።

በእንተ ትሩፋን ።

፩ ሰብሕዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ኵልክሙ ፡ አሕዛብ ።
ወይሴብሕዎ ፡ ኵሎሙ ፡ ሕዝብ ።
፪ እስመ ፡ ጸንዐት ፡ ምሕረቱ ፡ ላዕሌነ ።
ወጽድቁሰ ፡ ለእግዚአብሔር ። ይሄሉ ፡ ለዓለም ።



እናንተ ። ሰማይንና ፡ ምድርን ፡ ለሠራ ፡ ለእግዚ
አብሔር ፡ የተባረካችሁ ፡ ናችሁ ። ፳፫
የሰማያት ፡ ሰማይ ለእግዚአብሔር ፡ ነው ፡ ፳፬
ምድርን ፡ ግን ፡ ለሰው ፡ ልጆች ፡ ሰጣት ።
አቤቱ፡ሙታን ፡ የሚያመሰግኑህ ፡ አይደሉም ፤ ፳፭
ወደ፡መቃብርም ፡ የሚወርዱ ፡ አያመሰግኑህም ።
እኛ፡ሕያዋን፡ግን፡ከዛሬ፡ጀምሮ፡እስከ፡ዘላለም ፡ ፳፮
እግዚአብሔርን ፡ እንባርካለን ።
ሃሌ ፡ ሉያ ።

መዝሙር ፡ ፻፲፬ ።

ስለ ፡ ሕዝቅያስ ።

ሃሌ ፡ ሉያ ፤
እግዚአብሔር ቃልመናዬን ፡ ድምፅ ፡ ሰምቷልና ፡ ወደድሁት ። ፩
ጆሮውን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አዘንብሏልና ፡ ፪
በዘመኔ ፡ ሁሉ ፡ እጠራዋለሁ ።
የሞት፡ጣር ፡ ያዘኝ ፡ የሲኦልም ፡ ሕማም ፡ አገኘኝ ፤ ፫
ጭንቀትንና ፡ መከራን ፡ አገኘሁ ።
የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ ጠራሁ ፡ ፬
አቤቱ ፡ ነፍሴን ፡ አድናት ።
እግዚአብሔር ፡ መሐሪና ፡ ጻድቅ ፡ ነው ፡ ፭
አምላካችንም ፡ ይቅር ፡ ባይ ፡ ነው ።
እግዚአብሔር ፡ የዋሃንን ፡ ይጠብቃል ፡ ፮
ተቸገርሁ ፡ እርሱም ፡ አዳነኝ ።
ነፍሴ ፡ ሆይ ፡ ወደ ፡ ዕረፍትሽ ፡ ተመለሽ ፡ ፯
እግዚአብሔር ፡ መልካም ፡ አድርጎልሻልና ።
ነፍሴን ፡ ከሞት ፡ ዓይኔንም ፡ ከዕንባ ፡ ፰
እግሬንም ፡ ከመሰናከል ፡ አድኖአልና ።
በሕያዋን ፡ አገር ፡በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እሄዳለሁ ። ፱

መዝሙር ፡ ፻፲፭ ።

ስለ ፡ ሕዝቅያስ ።

አመንሁ ፡ ስለዚህም ፡ ተናገርሁ ፡ ፩
እኔም ፡ እጅግ ፡ ተቸገርሁ ።
እኔም ፡ ከድንጋጤ ፡ የተነሣ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ሐሰተኛ ፡ ነው ፡ አልሁ ፡ ፪
ስለ አደረገልኝ ሁሉ ፈንታ ለእግዚአብሔር ፡ ምንን እመልሳለሁ ? ፫
የመድኃኒትን ፡ ጽዋ ፡ እቀበላለሁ ፡ ፬
የእግዚአብሔርንም ፡ ስም ፡ እጠራለሁ ።
በሕዝቡ ሁሉ ፊት ስእለቴን ለእግዚአብሔር ፡ እፈጽማለሁ ። ፭
የቅዱሳኑ ፡ ሞት ፡ በእግዚአብሔር ፊት ፡ የከበረ ፡ ነው ። ፮
አቤቱ ፡ እኔ ፡ ባሪያህ ፡ ነኝ ፡ ፯
ባሪያህ ፡ ነኝ ፡ የሴት ፡ ባሪያህም ፡ ልጅ ፡ ነኝ ፡
ሰንሰለቴን ፡ ቆረጥህ ።
ለአንተ ፡ የምስጋና ፡ መሥዋዕትን ፡ ዕሠዋለሁ ፡ ፰
የእግዚአብሔርንም ፡ ስም ፡ እጠራለሁ ።
በሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ስእለቴን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ፱
እፈጽማለሁ ።
በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አደባባይ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ፲
ሆይ ፡ በመካከልሽም ።
ሃሌ ፡ ሉያ ።

መዝሙር ፡ ፻፲፮ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

ሃሌ ፡ ሉያ ።
አሕዛብ ፡ ሁላችሁ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑት ፡ ፩
ወገኖችም ፡ ሁሉ ፡ ያመስግኑት ።
ምሕረቱ ፡ በእኛ ፡ ላይ ፡ ጸንታለችና ፡ ፪
የእግዚአብሔርም ፡ እውነት ፡ ለዘላለም ፡ ትኖራለች ።
ሃሌ ፡ ሉያ ።

መዝሙር ፡ ፻፲፯ ።

በእንተ ትሩፋን ።

፩ ግነዩ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እስመ ፡ ኄር ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
ንግሩ ፡ ቤተ ፡ እስራኤል ፡ ከመ ፡ ኄር ።
፪ ከመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
ንግሩ ፡ ቤተ ፡ አሮን ፡ ከመ ፡ ኄር ።
፫ ከመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
ንግሩ ፡ ኵልክሙ ፡ እለ ፡ ትፈርህዎ ፡ ለእግዚ
አብሔር ከመ ፡ ኄር ።
፬ ከመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፭ ሶበ ፡ ተመንደብኩ ፡ ጸዋዕክዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
ሰምዐኒ ፡ ወአርሐበ ፡ ሊተ ።
፮ እግዚአብሔር ይረድአኒ ፤ ኢይፈርህ ፡ ዕጓለ ፡ እመ
ሕያው ፡ ምንተ ፡ ይሬስየኒ ።
፯ እግዚአብሔር ይረድአኒ፤ወአነ፡እሬእዮሙ፡ለጸላእትየ ።
፰ ይኄይስ ፡ ተአምኖ ፡ በእግዚአብሔር ፡ እምተአምኖ ፡
በዕጓለ ፡ እመሕያው ።
፱ ይኄይስ ፡ ተሰፍዎ ፡ በእግዚአብሔር ፡ እምተሰፍዎ ፡
በመላእክት ።
፲ ኵሎሙ ፡ አሕዛብ ፡ ዐገቱኒ ።
ወበስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሞዕክዎሙ ።
፲፩ ዐጊተስ ፡ ዐገቱኒ ።
ወበስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ሞዕክዎሙ ።
፲፪ ዐገቱኒ ፡ ከመ ፡ ንህብ ፡ መዓረ ።
ወነዱ ፡ ከመ ፡ እሳት ፡ ውስተ ፡ አሥዋክ ።
ወበስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሞዕክዎሙ ።
፲፫ ተንተንኩ ፡ ለወዲቅ ፡ ወእግዚአብሔር ፡አንሥአኒ ።
፲፬ ኀይልየኒ ፡ ወዝክርየኒ ፡ እግዚአብሔር ።
ወውእቱ ፡ ኮነኒ ፡መድኀኒየ ።
፲፭ ቃለ ፡ ትፍሥሕት ፡ ውስተ ፡ አብያቲሆሙ ፡ ለጻድቃን።
የማነ ፡ እግዚአብሔር ፡ ገብረት ፡ ኀይለ ።
፲፮ የማነ ፡ እግዚአብሔር ፡ አልዐለተኒ ።
የማነ ፡ እግዚአብሔር ፡ ገብረት ፡ ኀይለ ።
፲፯ ኢይመውት ፡ ዘእንበለ ፡ ዘእሐዩ ።
ወእነግር ፡ ግብሮ ፡ ለእግዚአብሔር ።
፲፰ ገሥጾሰ ፡ ገሠጸኒ ፡ እግዚአብሔር ።
ወለሞትሰ ፡ ባሕቱ ፡ ኢመጠወኒ ።
፲፱ አርኅዉ ፡ ሊተ ፡ አናቅጸ ፡ ጽድቅ ።
እባእ ፡ ውስቴቶን ፡ ወእግነይ ፡ለእግዚአብሔር ።
፳ ዛ ፡ አንቀጽ ፡ እንተ ፡እግዚአብሔር ።
ጻድቃን ፡ ይበውኡ ፡ ውስቴታ ።
፳፩ እገኒ ፡ ለከ ፡ እግዚእ ፡ እስመ ፡ ሰማዕከኒ ።
ወኮንከኒ ፡ መድኀኒየ ።
፳፪ እብን ፡ ዘመነንዋ ፡ ነደቅት ።
ወይእቲ ፡ ኮነት ፡ ውስተ ፡ ርእሰ ፡ ማእዘንት ።
፳፫ እምኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡ ኮነት ፡ ዛቲ ።
ወነካር ፡ ይእቲ ፡ ለአዕይንቲነ ።
፳፬ ዛቲ ፡ ዕለት ፡ እንተ ፡ ገብረ ፡ እግዚአብሔር ።
ንትፌሣሕ ፡ ወንትሐሠይ ፡ ባቲ ።
፳፭ ኦ ፡ እግዚኦ ፡ አድኅንሶ ።
ኦ ፡ እግዚኦ ፡ ሠርሕሶ ።
፳፮ ቡሩክ ፡ ዘይመጽእ ፡ በስመ ፡ እግዚአብሔር ።
ባረክናክሙ ፡ እምቤተ ፡ እግዚአብሔር ።
፳፯ እግዚአብሔር፡ እግዚእ ፡ አስተርአየ ፡ ለነ ።
ግበሩ፡በዓለ፡በትፍሥሕት ፡ በኀበ፡እለ ፡ ያስተሐምምዎ ።
እስከ ፡ አቅርንቲሁ ፡ ለምሥዋዕ ።



መዝሙር ፡ ፻፲፯ ።
ስለ ፡ ትሩፋን ።

ሃሌ ፡ ሉያ ።
እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ፡ ቸር ፡ ነውና ፡ ፩
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ናትና ።
ቸር ፡ እንደሆነ ፡ ምሕረቱም ፡ ለዘላለም ፡ እንደ፡ሆነች ፡ ፪
የእስራኤል ፡ ቤት ፡ አሁን ፡ ይንገሩ ።
ቸር፡ እንደ ፡ ሆነ፡ ምሕረቱም፡ ለዘላለም፡ እንደ፡ ሆነች ፡ ፫
የአሮን ፡ ቤት ፡ አሁን ፡ ይንገሩ ።
ቸር፡ እንደ፡ ሆነ፡ ምሕረቱም፡ ለዘላለም፡ እንደ፡ ሆነች ፡ ፬
እግዚአብሔርን ፡ የሚፈሩ ፡ ሁሉ ፡ አሁን ፡ ይንገሩ ።
በተጨነቅሁ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ጠራሁት ፡ ፭
ሰማኝ ፡ አሰፋልኝም ።
እግዚአብሔር ፡ ረዳቴ ፡ ነው ፡ አልፈራም ፡ ሰው ፡ ምን ፮
ያደርገኛል ?
እግዚአብሔር ፡ ረዳቴ ፡ ነው ፡ እኔም ፡ ጠላቶቼን ፡ አያ ፯
ቸዋለሁ ።
በሰው ፡ ከመታመን ፡ ይልቅ ፡ በእግዚአብሔር ፡ መታ ፰
መን ፡ ይሻላል ።
በገዥዎች ፡ ተስፋ ፡ ከማድረግ ፡ ይልቅ ፤ በእግዚአ ፱
ብሔር ፡ ተስፋ ፡ ማድረግ ፡ ይሻላል ።
አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ከበቡኝ ፡ ፲
በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ አሸነፍኋቸው ።
መክበቡንስ ፡ ከበቡኝ ፡ ፲፩
በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ አሸነፍኋቸው ።
ንብ ፡ ማርን ፡ እንዲከብ ፡ ከበቡኝ ፡ ፲፪
እሳትም ፡ በእሾህ ፡ ውስጥ ፡ እንዲነድ ፡ ነደዱ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ አሸነፍኋቸው ።
ገፉኸኝ ፡ ለመውደቅም፡ ተንገደገድሁ ። ፲፫
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ አነሣኝ ።
ኀይሉም ፡ ዝማሬዬም ፡እግዚአብሔር ፡ ነው ፡ ፲፬
እርሱም ፡ መድኃኒት ፡ ሆነልኝ ።
የእልልታና የመድኀኒት ድምፅ በጻድቃን ድንኳን ነው፡ ፲፭
የእግዚአብሔር ፡ ቀኝ ፡ ኀይልን ፡ አደረገች ።
የእግዚአብሔር ፡ ቀኝ ፡ ከፍ፡ከፍ ፡ አደረገችኝ ፡ ፲፮
የእግዚአብሔር ፡ ቀኝ ፡ ኀይልን ፡ አደረገች ።
አልሞትም ፡ በሕይወት ፡ እኖራለሁ ፡ እንጂ ፡ ፲፯
የእግዚአብሔርንም ፡ ሥራ ፡ እናገራለሁ ።
መገሠጽንስ ፡ እግዚአብሔር ፡ ገሠጸኝ ፡ ፲፰
ለሞት ፡ ግን ፡ አሳልፎ ፡ አልሰጠኝም ።
የጽድቅን ፡ ደጆች ፡ ክፈቱልኝ ፡ ፲፱
ወደ፡እነርሱ ፡ ገብቼ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰግናለሁ።
ይህች ፡ የእግዚአብሔር ፡ ደጅ ፡ ናት ፡ ፳
ወደ ፡ እርሷ፡ ጻድቃን ፡ ይገባሉ ።
ሰምተኸኛልና ፡ ፳፩
መድኃኒትም ፡ ሆንኸኛልና ፡ አመሰግንሃለሁ ።
አናጢዎች ፡ የናቁት ፡ ድንጋይ ፡ ፳፪
እርሱ ፡ የማዕዘንት ፡ ራስ ፡ ሆነ ።
ይህች ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ሆነች ፡ ፳፫
ለዓይናችንም ፡ ድንቅ ፡ ናት ።
እግዚአብሔር ፡ የሠራት ፡ ቀን ፡ ይህች ፡ ናት ፳፬
ሐሤትን ፡ እናድርግ ፡ በእርሷም ፡ ደስ ፡ ይበለን ።
አቤቱ ፡ እባክህ ፡ አሁን ፡ አድን ፡ ፳፭
አቤቱ ፡ እባክህ ፡ አሁን ፡ አቅና ።
በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ የሚመጣ ፡ ቡሩክ ፡ ነው ። ፳፮
ከእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ መረቅናችሁ ።
እግዚአብሔር ፡ አምላክ ፡ ነው ፡ ለእኛም ፡ በራልን ፡ ፳፯
እስከ ፡ መሠዊያው ፡ ቀንዶች ፡ ድረስ ።
የበዓሉን ፡ መሥዋዕት ፡ በገመድ ፡ እሰሩት ።

፳፰ አምላኪየ ፡ አንተ ፡ እገኒ ፡ ለከ ።
አምላኪየ ፡ አንተ ፡ ወአሌዕለከ ።
እገኒ ፡ ለከ ፡ እግዚኦ ፡ እስመ ፡ ሰማዕከኒ ።
ወኮንከኒ ፡ መድኀኒየ ።
፳፱ ግነዩ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እስመ ፡ ኄር ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።

መዝሙር ፡ ፻፲፰ ።

በእንተ ትሩፋን ።

አሌፍ ፡ ብሂል ፡ አብ ፡ ፈጣሬ ፡ ኵሉ ፡ ዓለም ።
፩ አሌፍ ፡ ብፁዓን ፡ እለ ፡ ንጹሓን ፡ በፍኖቶሙ ፡
ወእለ ፡ የሐውሩ ፡ በሕገ ፡ እግዚአብሔር ።
፪ ብፁዓን ፡ እለ ፡ የኀሡ ፡ ስምዖ ።
ወበኵሉ ፡ ልቦሙ ፡ የኀሥሥዎ ።
፫ እለሰ ፡ ይገብሩ ፡ ዓመፃ ፡ ፍኖተ ፡ ዚአሁ ፡ ኢሖሩ ።
፬ አንተ ፡ አዘዝከ ፡ ይዕቀቡ ፡ ትእዛዘከ ፡ ፈድፋደ ።
ይረትዕሰ ፡ ይርታዕ ፡ ፍኖትየ ።
፭ ከመ ፡ እዕቀብ ፡ ኵነኔከ ።
ውእተ ፡ ጊዜ ፡ ኢይትኀፈር ።
፮ በርእየ ፡ ኵሉ ፡ ትእዛዝከ ።
እገኒ ፡ ለከ ፡ እግዚኦ ፡ በልብ ፡ ርቱዕ ።
፯ ሶበ ፡ ተመሀርኩ ፡ ኵነኔ ፡ ጽድቅከ ።
፰ ወአዐቅብ ፡ ኵነኔከ ።
ወኢትግድፈኒ ፡ ለዝሉፉ ።

ቤት ፡ ብሂል ፡ ባዕል ፡ እግዚአብሔር ።

፱ ቤት ፡ በምንት ፡ ያረትዕ ፡ ወሬዛ ፡ ፍኖቶ ።
በዐቂበ ፡ ነቢብከ ።
፲ ወበኵሉ ፡ ልብየ ፡ ኀሠሥኩከ ።
ኢታርኅቀኒ ፡ እምትእዛዝከ ።
ውስተ ፡ ልብየ ፡ ኀባእኩ ፡ ነቢበከ ።
፲፩ ከመ ፡ ኢየአብስ ፡ ለከ ።
፲፪ ቡሩክ ፡ አንተ ፡ እግዚኦ ፤ ወምሀረኒ ፡ ኵነኔከ ።
፲፫ በከናፍርየ ፡ ነገርኩ ፡ ኵሎ ፡ ኵነኔ ፡ አፉከ ።
በፍኖተ ፡ ስምዕከ ፡ ተፈሣሕኩ ።
፲፬ ከመ ፡ ዘበኵሉ ፡ ብዕል ።
፲፭ ወእዛዋዕ ፡ በትእዛዝከ ።
ወእኄሥሥ ፡ ፍናዊከ ።
፲፮ ወአነብብ ፡ ትእዛዛቲከ ። ወኢይረስዕ ፡ ቃለከ ።

ጋሜል ፡ ብሂል ፡ ግሩም ፡ እግዚአብሔር ።

፲፯ ጋሜል ፡ ዕስዮ ፡ ለገብርከ ።
ከመ ፡ እሕየው ፡ ወእዕቀብ ፡ ነቢበከ ።
፲፰ ክሥቶን ፡ ለአዕይንትየ ፡ ወእርአይ ።
መድምምከ ፡ እምሕግከ ።
፲፱ ፈላሲ ፡ አነ ፡ ውስተ ፡ ምድር ።
ኢትኅባእ ፡ እምኔየ ፡ ትእዛዘከ ።
፳ አፍቀረት ፡ ነፍስየ ፡ ወፈተወት ።
ኵነኔከ ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ።
፳፩ ገሠጽከሙ ፡ ለዕቡያን ።
ርጉማን ፡ እለ ፡ ይትገሐሡ ፡ እምትእዛዝከ ።
አእትት ፡ እምኔየ ፡ ጽዕለተ ፡ ወኀሳረ ።
፳፪ እስመ ፡ ትእዛዘከ ፡ ኀሠሥኩ ።
፳፫ እስመ ፡ ነበሩ ፡ መላእክት ፡ ወኪያየ ፡ ሐመዩ ።
ወገብርከሰ ፡ ይዛዋዕ ፡ በኵነኔከ ።



አንተ ፤ አምላኬ ፡ ነህ ፡ አመሰግንሃለሁ ፡ ፳፰
አንተ ፡ አምላኬ ፡ ነህ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደርግሃለሁ ፡
ሰምተኸኛልና ፡
መድኃኒትም ፡ ሆንኸኛልና ፡ አመሰግንሃለሁ።
እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ ፡ ቸር ፡ ነውና ፡ ፳፱
ምሕረቱም ፡ ለዘላለም ፡ ናትና ።

መዝሙር ፡ ፻፲፰ ።
አሌፍ ፡ ማለት ።

ዓለምን ፡ ከንቱ ፡ ካለመኖር ፡ ወደ ፡ መኖር ፡ አምጥቶ ፡ የፈጠረ ፡
እግዚአብሔር ፡ ማለት ፡ ነው ።

አሌፍ ፡ በመንገዳቸው ፡ ንጹሐን ፡ የሆኑ ። ፩
በእግዚአብሔርም ፡ ሕግ ፡ የሚሄዱ ፡ ምስጉኖች ፡ ናቸው።
ምስክሩን ፡ የሚፈልጉ ፡ ፪
በፍጹም ፡ ልብም ፡ የሚሹት ፡ ምስጉኖች ፡ ናቸው ።
ዓመፅንም ፡ አያደርጉም ፡ በመንገዶቹም ፡ ይሄዳሉ ፡ ፫
ትእዛዛትህን ፡ ፈጽመን ፡ እንጠብቅ ፡ ዘንድ ፡ አንተ ፡ አዘዝህ ፡ ፬
ሥርዓትህን ፡ ለመጠበቅ ፡ ፭
መንገዶቼ ፡ ይቃኑ ፡ ዘንድ ፡ እወድ ፡ ነበር ።
ትእዛዝህን ፡ ስመለከት ፡ ፮
በዚያን ፡ ጊዜ ፡ አላፍርም ።
አቤቱ ፡ የጽድቅህን ፡ ፍርድ ፡ ስማር ፡ ፯
በቅን ፡ ልብ ፡ አመሰግንሃለሁ ።
ሥርዓትህን ፡ እጠብቃለሁ ፡ ፰
በፍጹም ፡ አትጣለኝ ።

ቤት ፡ ማለት።

እግዚአብሔር ፡ ሁሉን መስጠት የሚችል ቸር ለጋስ ባለጸጋ ማለት ነው ።
ቤት ። ጐልማሳ ፡ መንገዱን ፡ በምን ፡ ያነጻል ? ፱
ቃልህን ፡ በመጠበቅ ፡ ነው ፡ እንጂ ።

በፍጹም ፡ ልቤ ፡ ፈለግሁህ ፡ ፲
ከትእዛዝህ ፡ አታርቀኝ ።
አንተን ፡ እንዳልበድል ፡ ፲፩
ነገርህን ፡ በልቤ ፡ ሰወርሁ ።
አቤቱ ፡ አንተ ፡ ቡሩክ ፡ ነህ ፡ ፲፪
ሥርዓትህን ፡ አስተምረኝ ።
ያፍህን ፡ ፍርድ ፡ ሁሉ ፡ በከንፈሬ ፡ ነገርሁ ፡ ፲፫
እንደ ፡ ብልጽግና ፡ ሁሉ ፡ ፲፬
በምስክርህ ፡ መንገድ ፡ ደስ ፡ አለኝ ።
በትእዛዝህ ፡ እነጋገራለሁ ፡ ፲፭
መንገድህንም ፡ እፈልጋለሁ ።
በትእዛዝህ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፡ ፲፮
ቃልህንም ፡ አልረሳም ።

ጋሜል ፡ ማለት ፡

እግዚአብሔር ፡ ሊመረመር የማይቻል ግሩም ድንቅ ማለት ነው ።
ጋሜል ። ለባሪያህ ፡ መልካምን ፡ አድርግ ፡ ፲፯
ሕያውም ፡ እሆናለሁ ፡ ነገርህንም ፡ እጠብቃለሁ ።
ዓይኖቼን ፡ ክፈት ፡ ፲፰
ከሕግህም ፡ ተአምራትህን ፡ አያለሁ ።
እኔ ፡ በምድር ፡ እንግዳ ፡ ነኝ ፡ ፲፱
ትእዛዛትህን ፡ ከእኔ ፡ አትሰውር ።
ነፍሴ ፡ ሁልጊዜ ፡ ፍርድህን ፡ እጅግ ፡ ናፈቀች ፡ ፳
ከትእዛዛትህ ፡ የሳቱትን ፡ ትዕቢተኞችንና ፡ ርጉማንን ፡ ፳፩
ዘለፍክ ፡
ምስክርህን ፡ ፈልጌአለሁና ፡ ፳፪
ስድብንና ፡ ነውርን ፡ ከእኔ ፡ አርቅ ።
አለቆች ፡ ደግሞ ፡ ተቀምጠው ፡ እኔን ፡ አሙኝ ፡ ፳፫
ባሪያህ ፡ ግን ፡ በሕግህ ፡ ያስብ ፡ ነበር ።

፳፬ እስመ ፡ ስምዕከ ፡ ተምህርየ ፡ ውእቱ ።
ወምክርየኒ ፡ ኵነኔ ፡ ዚአከ ።

ዳሌጥ ፡ ብሂል ፡ ድልው ፡ እግዚአብሔር ።

፳፭ ዳሌጥ ፡ ጠግዐት ፡ ነፍስየ ፡ በምድር ።
ወአሕይወኒ ፡ በከመ ፡ ነቢብከ ።
፳፮ ነገርኩ ፡ ፍናዊከ ፡ ወሰምዐከኒ ።
ወምሀረኒ ፡ ኵኔነከ ።
፳፯ ፍኖተ ፡ ጽድቅከ ፡ አለብወኒ ።
ወእዛዋዕ ፡ በመንክርከ ።
፳፰ ደቀሰት ፡ ነፍስየ ፡ እምኀዘን ።
አጽንዐኒ ፡ በነቢብከ ።
፳፱ ፍኖተ ፡ ዐመፃ ፡ አርኅቅ ፡ እምኔየ ።
ወበሕግከ ፡ ተሣሀለኒ ።
፴ ፍኖተ ፡ ጽድቅከ ፡ አብደርኩ ።
ወኵነኔከስ ፡ ኢረሳዕኩ ።
፴፩ ተለውኩ ፡ ስምዐከ ፡ እግዚእ ፤ ኢታስተኀፍረኒ ።
ፍኖተ ፡ ትእዛዝከ ፡ ሮጽኩ ።
፴፪ ሶበ ፡ አርሐብከ ፡ ለልብየ ።

ሄ ፤ ብሂል ፡ ህልው ፡ እግዚአብሔር ።

፴፫ ሄ ፤ ምህረኒ ፡ እግዚእ ፡ ፍኖተ ፡ ጽድቅከ ።
ወእኅሥሣ ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ።
፴፬ አለብወኒ ፡ ወእኅሥሥ ፡ ሕገከ ።
ወእዕቀብ ፡ በኵሉ ፡ ልብየ ።
፴፭ ምርሐኒ ፡ ፍኖተ ፡ ትእዛዝከ ።
እስመ ፡ ኪያሃ ፡ ፈቀድኩ ።
፴፮ ሚጥ ፡ ልብየ ፡ ውስተ ፡ ስምዕከ ።
ወአኮ ፡ ውስተ ፡ ትዕግልት ።
፴፯ ሚጠን ፡ ለአዕይንትየ ፡ ከመ ፡ ኢይርአያ ፡ ከንቶ ።
ወአሕይወኒ ፡ በፍኖትከ ።
፴፰ አቅም ፡ ለገብርከ ፡ ዘነበብኩ ፡ ውስተ ፡ ነቢብከ ።
እእትት ፡ እምኔየ ፡ ጽዕለተ ፡ ዘተሐዘብኩ ።
፴፱ እስመ ፡ ሠናይ ፡ ኵነኔከ ።
፵ ናሁ ፡ ፈተውኩ ፡ ትእዛዘከ ።
ወአሕይወኒ ፡ በጽድቅከ ።

ዋው ፡ ብሂል ፡ ዋሕድ ፡ እግዚአብሔር ።

ዋው ፤ ይምጻእ ፡ ላዕሌየ ፡ ምሕረትከ ፡ እግዚእ ።
፵፩ እግዚእ ፡ አድኅኖትከ ፡ በከመ ፡ ነቢብከ ።
አውሥአሙ ፡ ቃለ ፡ ለእለ ፡ ይጼዕሉኒ ።
፵፪ እስመ ፡ ተወከልኩ ፡ በቃልከ ።
ኢታእትት ፡ ቃለ ፡ ጽድቅ ፡ እምአፉየ ፡ ለግሙራ ።
፵፫ እስመ ፡ ተወከልኩ ፡ በኵነኔከ ።
ወአዐቅብ ፡ ሕገከ ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ።
፵፬ ለዓለም ፡ ወለዓለመ ፡ ዓለም ።
፵፭ ወአሐውር ፡ በፋሐ ። እስመ ፡ ትእዛዘከ ፡ ኀሠሥኩ ።
፵፮ ወእነግር ፡ ስምዐከ ፡ በቅድመ ፡ ነገሥት ፤ ወኢይት
ኀፈር ።
፵፯ ወእነብብ ፡ ትእዛዘከ ፡ ዘአፍቀርኩ ፡ ጥቀ ።
፵፰ ወአነሥእ ፡ እደውየ ፡ ኀበ ፡ ትእዛዝከ ፡ ዘአፍቀርኩ ።
ወእዛዋዕ ፡ በትእዛዝከ ።

ዛይ ፡ ብሂል ፡ ዝኩር ፡ እግዚአብሔር ።

፵፱ ዛይ ፤ ተዘከር ፡ ቃለከ ፡ ዘአሰፈውኮ ፡ ለገብርከ ።
ወይእቲ ፡ አስተፍሥሐተኒ ፡ በሕማምየ ።



ምስክርህም ፡ አሳቤ ፡ ነው ፡ ፳፬
ሥርዓትህም ፡ መካሬ ፡ ነው ።
ዳሌጥ ፡ ማለት ።
እግዚአብሔር በጌትነቱ ዙፋን ለዘለዓለም ይኖራል ማለት ነው ።

ዳሌጥ ፡ ነፍሴ ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ተጠጋች ፡ ፳፭
በነገርህ ፡ ሕያው ፡ አድርገኝ ።
መንገድህን ፡ ነገርሁ ፡ ሰማኸኝም ፡ ፳፮
ሥርዓትህን ፡ አስተምረኝ ።
የሥርዓትህን ፡ መንገድ ፡ እንዳስተውል ፡ አድርገኝ ፡ ፳፯
በተአምራትህም ፡ እጫወታለሁ ።
ከኀዘን ፡ የተነሣ ፡ ነፍሴ ፡ አንቀላፋች ፡ ፳፰
በነገርህ ፡ አጠንክረኝ ።
የዓመፅን ፡ መንገድ ፡ ከእኔ ፡ አርቅ ፡ ፳፱
በሕግህም ፡ ይቅር ፡ በለኝ ።
የእውነትህን ፡ መንገድ ፡ መረጥሁ ፡ ፴
ፍርድህንም ፡ አልረሳሁም ።
ምስክርህን ፡ ተጠጋሁ ፡ ፴፩
አቤቱ ፡ አታሳፍረኝ ።
ልቤን ፡ በአሰፋኸው ፡ ጊዜ ፡ ፴፪
በትእዛዝህ ፡ መንገድ ፡ ሮጥሁ ።
ሄ ፡ ማለት ።
እግዚአብሔር በአንድነቱ በሦስትነቱ ጸንቶ ለዘለዓለም ይኖራል ማለት ነው ።

ሄ ፤ አቤቱ ፡ የሥርዓትህን ፡ መንገድ ፡ አስተምረኝ ፡ ፴፫
ሁል ፡ ጊዜም ፡ እፈልገዋለሁ ።
እንዳስተውል ፡ አድርገኝ ፡ ሕግህንም ፡ እፈልጋለሁ ፡ ፴፬
በፍጹም ፡ ልቤም ፡ እጠብቀዋለሁ ።
እርሷን ፡ ወድጃለሁና ፡ የትእዛዝህን ፡ መንገድ ምራኝ ፡ ፴፭
ልቤን ፡ ወደ ፡ ምስክርህ ፡ አዘንብል ፡ ፴፮
ወደ ፡ ስስትም ፡ አይሁን ።
ከንቱ ፡ ነገርን ፡ እንዳያዩ ፡ ዓይኖቼን ፡ መልስ ፡ ፴፯
በመንገድህ ፡ ሕያው ፡ አድርገኝ ።
እንዲፈራህ ፡ ባሪያህን ፡ በቃልህ ፡ አጽና ፡ ፴፰
ፍርድህ ፡ መልካም ፡ ናትና ፡ ፴፱
የጠረጠርሁትን ፡ ስድብ ፡ ከእኔ ፡ አርቅ ።
እነሆ ፡ ትእዛዝህን ፡ ናፈቅሁ ፡ ፵
በጽድቅህ ፡ ሕያው ፡ አድርገኝ ።
ዋው ፡ ማለት ።
እግዚአብሔር ፡ በመንግሥት በሥልጣን በአገዛዝ በባሕርይ አንድ አምላክ የሆነ ማለት ነው ።

ዋው ፡ አቤቱ ፡ እንደ ፡ ቃልህ ፡ ፵፩
ምሕረትህና ፡ መድኃኒትህ ፡ ይምጡልኝ ።
በቃልህ ፡ ታምኛለሁና ፡ ፵፪
ለሚሰድቡኝ ፡ በነገር ፡ እመልስላቸዋለሁ ።
በፍርድህም ፡ ታምኛለሁና ፡ ፵፫
የእውነትን ፡ ቃል ፡ ከአፌ ፡ ፈጽመህ ፡ አታርቅ ።
ለዘላለም ፡ ዓለም ፡ ፵፬
ሁል ፡ ጊዜ ፡ ሕግህን ፡ እጠብቃለሁ ።
ትእዛዛትህንም ፡ ፈልጌአለሁና ፡ ፵፭
እስፍቼ ፡ እሄዳለሁ ።
በነገሥታት ፡ ፊት ፡ ምስክርህን ፡ እናገራለሁ ፡ አላፍርምም ። ፵፮
እጅግም ፡ በወደድኋቸው ፡ በትእዛዛትህ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ። ፵፯
እጄንም ፡ ወደ ፡ ወደድኋቸው ፡ ወደ ፡ ትእዛዛትህ ፡ አነሣለሁ ። ፵፰
በሥርዓትህም ፡ እጫወታለሁ ።
ዛይ ፡ ማለት ።
እግዚአብሔር ፡ በሥራው ፡ ሁሉ ፡ እየታሰበ ፡ ሲመሰገን ፡ የሚኖር ፡ ፈጣሪ ፡ ማለት ፡ ነው ።

ዛይ ፤ ለባሪያህ ፡ ተስፋ ፡ ያስደረግኸውን ፡ ቃልህን ፡ አስብ ፡ ፵፱

፵ እስመ ፡ ቃልከ ፡ አሕየወኒ ።
፵፩ ዕቡያን ፡ ዐመፁ ፡ ፈድፋደ ።
ወእምሕግከሰ ፡ ኢተግሕሥኩ ።
፵፪ ተዘከርኩ ፡ ፍትሐከ ፡ ዘእምዓለም ።
ወተፈሣሕኩ ፡ እግዚኦ ።
፵፫ ኀዘን ፡ አኀዘኒ ፡ እምኃጥአን ። እለ ፡ ኀደጉ ፡ ሕገከ ።
፵፬ መዝሙረ ፡ ኮነኒ ፡ ኩነኔከ ።
በብሔር ፡ በኀበ ፡ ፈለስኩ ።
፵፭ ተዘከርኩ ፡ በሌሊት ፡ ስመከ ፡ እግዚኦ ።
ወዐቀብኩ ፡ ሕገከ ። ወይእቲ ፡ ኮነተኒ ።
፵፮ እስመ ፡ ኵነኔከ ፡ ኀሠሥኩ ።

ሔት ፡ ብሂል ፡ ሕያው ፡ እግዚአብሔር ።

፵፯ ሔት ፤ ክፍልየ ፡ እግዚአብሔር ፡
ወእቤ ፡ ይዕቀቡ ፡ ሕገከ ።
፵፰ ሰአልኩ ፡ ገጸከ ፡ እግዚኦ ፡ በኵሉ ፡ ልብየ ።
ተሣሀለኒ ፡ በከመ ፡ ነቢብከ ።
፵፱ ወሐለይኩ ፡ በእንተ ፡ ፍናዊከ ።
ሜጥኩ ፡ እግርየ ፡ ውስተ ፡ ስምዕከ ።
አጥባዕኩ ፡ ወኢናፈቅ ።
፶ ለዐቂበ ፡ ትእዛዝከ ።
፶፩ አሕባለ ፡ ኃጥአን ፡ ተፃፈራ ፡ ላዕሌየ ።
ወሕገከሰ ፡ ኢረሳእኩ ።
መንፈቀ ፡ ሌሊት ፡ እትነሣእ ።
፶፪ ከመ ፡ እግነይ ፡ ለከ ፡ በእንተ ፡ ኵነኔ ፡ ጽድቅከ ።
፶፫ ከማሆሙ ፡ አነ ፡ ለኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይፈርሁከ ።
ወእለ ፡ የዐቅቡ ፡ ትእዛዘከ ።
፶፬ ሣህልከ ፡ እግዚኦ ፡ መልአ ፡ ምድረ ።
ወምህረኒ ፡ ኵነኔከ ።

ጤት ፡ ብሂል ፡ ጠቢብ ፡ እግዚአብሔር ።

፶፭ ጤት ሠናይት ፡ ገበርከ ፡ ላዕለ ፡ ገብርከ ።
እግዚኦ ፡ በከመ ፡ ቃልከ ።
ሠናይት ፡ ምክረ ፡ ወጥበበ ፡ ምህረኒ ።
፶፮ እስመ ፡ ተአመንኩ ፡ በትእዛዝከ ።
፶፯ ወእንበ ፡ ዘእንበለ ፡ እሕምም ፡ ነሳሕኩ ።
ወበእንተዝ ፡ አነ ፡ ዐቀብኩ ፡ ነቢበከ ።
፶፰ ኄር ፡ አንተ ፡ እግዚኦ ።
ወበኂሩትከ ፡ ምህረኒ ፡ ኵነኔከ ።
፶፱ በዝኀ ፡ ላዕሌየ ፡ ዐመፃሆሙ ፡ ለዕቡያን ።
ወአንሰ ፡ በኵሉ ፡ ልብየ ፡ ኀሠሥኩ ፡ ትእዛዘከ ።
፷ ረግዐ ፡ ከመ ፡ ሐሊብ ፡ ልቦሙ ።
ወአንሰ ፡ አነብብ ፡ በሕግከ ።
ደለወኒ ፡ ዘአሕመምከኒ ።
፷፩ ከመ ፡ እእምር ፡ ኵነኔከ ።
ይኄይሰኒ ፡ ሕገ ፡ አፉከ ።
፷፪ እምእእላፍ ፡ ወርቅ ፡ ወብሩር ።

ዮድ ፡ ብሂል ፡ የማነ ፡ እግዚአብሔር ፤

፷፫ ዮድ ፤ እደዊከ ፡ ገብራኒ ፡ ወለሐኳኒ ።
አለብወኒ ፡ ወእትመሀር ፡ ትእዛዘከ ።
እለ ፡ ይፈርሁከ ፡ ይርእዩኒ ፡ ወይትፌሥሑ ።
፷፬ እስመ ፡ ተወከልኩ ፡ በነቢብከ ።
፷፭ አእመርኩ ፡ እግዚኦ ፡ ከመ ፡ ጽድቅ ፡ ኵነኔከ ።
ወበርቱዕ ፡ አሕመምከኒ ።
ይኩንኒ ፡ ምሕረትከ ፡ ከመ ፡ ያስተፍሥሐኒ ።



ቃልህ ፡ ሕያው ፡ አድርገኝልና ፡ ፵
ይህች ፡ በመከራዬ ፡ ደስ ፡ አሰኝችኝ ፡
ትዕቢተኞች ፡ እጅግ ፡ ዐመፁ ፡ ፵፩
እኔ ፡ ግን ፡ ከሕግህ ፡ አልራቅሁም ።
አቤቱ ፡ ከዘላለም ፡ የነበረውን ፡ ፍርድህን ፡ አሰብሁ ፡ ፵፪
አቤቱ ፡ ተጽናናሁም ።
ሕግህን፡ ከተዉ፡ከኃጢአተኞች፡የተነሣ፡ ኀዘን፡ያዘኝ ፡ ፵፫
በእንግድነቴ፡ አገር ፡ ሥርዓትህ ፡ መዝሙር፡ ሆነችኝ ፡ ፵፬
አቤቱ ፡ በሌሊት ፡ ስምህን ፡ አሰብሁ ፡ ፵፭
ሕግህንም ፡ ጠበቅሁ ።
ትእዛዛትህንም ፡ ፈልጌአለሁና ፡ ይህች ፡ ሆነችልኝ ። ፵፮

ሔት ፡ ማለት ።

እግዚአብሔር በመንግሥቱ ሽረት በባሕርዩ ኅልፈት የሌለበት ለዘለዓለም ሕያው የሆነ ማለት ፡ ነው ።

ሔት ፤ እግዚአብሔር ፡ ዕጣዬ ፡ ነው ፡ ፵፯
ትእዛዝህን ፡ እጠብቃለሁ ፡ አልሁ ።
በፍጹም ፡ ልቤ ፡ ወደ ፡ ፊትህ ፡ ተማለልሁ ፡ ፵፰
እንደ ፡ ነገርህ ፡ ይቅር ፡ በለኝ ።
ስለ ፡ መንገዶችህ ፡ አሰብሁ ፡ ፵፱
እግሬንም ፡ ወደ ፡ ምስክሮችህ ፡ መለስሁ ።
ትእዛዝህን ፡ ለመጠበቅ ፡ ጨከንሁ ፡ አልዘገየሁምም ፡ ፶
የኃጥአን ፡ ገመዶች ፡ ተተበተቡብኝ ፡ ፶፩
ሕግህን ፡ ግን ፡ አልረሳሁም ።
ስለ ፡ ጽድቅህ ፡ ፍርድ ፡ ፶፪
በእኩለ ፡ ሌሊት ፡ አመሰግንህ ፡ ዘንድ ፡ እነሣለሁ ።
እኔ ፡ ለሚፈሩህ ፡ ሁሉ ፡ ፶፫
ትእዛዝህንም ፡ ለሚጠብቁ ፡ ባልንጀራ ፡ ነኝ ።
አቤቱ ፡ ምሕረትህ ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ መላች ፡ ፶፬
ሥርዓትህን ፡ አስተምረኝ ።

ጤት ፡ ማለት ።

እግዚአብሔር ፡ ጥበብን የሚገልጽ ከጥበበኞች ይልቅ ፡ ጥበበኛ የሆነ አምላክ ማለት ነው ።

ጤት ፡ አቤቱ ፡ እንደ ፡ ቃልህ ፡ ፶፭
ለባሪያህ ፡ መልካም ፡ አደረግህ ።
በትእዛዝህ ፡ ታምኛለሁና ፡ ፶፮
መልካም ፡ ምክርንና ፡ ዕውቀትን ፡ አስተምረኝ ።
እኔ ፡ ሳልጨነቅ ፡ ሳትኩ ፡ ፶፯
አሁን ፡ ግን ፡ ነገርህን ጠበቅሁ ።
አቤቱ ፡ አንተ ፡ ቸር ፡ ነህ ፡ ፶፰
በቸርነትህም ፡ ሥርዓትህን ፡ አስተምረኝ ።
የትዕቢተኞች ፡ ዓመፅ ፡ በላዬ ፡ በዛ ፡ ፶፱
እኔ ፡ ግን ፡ በፍጹም ፡ ልቤ ፡ ትእዛዝህን ፡ እፈልጋለሁ ።
ልባቸው ፡ እንደ ፡ ወተት ፡ እረጋ ፡ ፷
እኔ ፡ ግን ፡ በሕግህ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ።
ሥርዓትህን ፡ እማር ፡ ዘንድ ፤ ፷፩
ያስጨነቅኸኝ ፡ መልካም ፡ ሆነልኝ ።
ከአእላፋት ፡ ወርቅና ፡ ብር ፡ ይልቅ ፤ ፷፪
የአፍህ ፡ ሕግ ፡ ይሻለኛል ።

ዮድ ፡ ማለት ።

በእግዚአብሔር ፡ ቀኝ ፡ ያለ ፡ እሱ ፡ ኃይልና ፡ ጽኑ ፡ የሆነ ፡ ማለት ፡ ነው ።

ዮድ ፤ እጆችህ ፡ ሠሩኝ ፡ አበጃጁኝም ። ፷፫
እንዳስተውል ፡ አድርገኝ ፡ ትእዛዛትህንም ፡ እማራለሁ ።
በነገርህ ፡ ታምኛለሁ ፡ ፷፬
የሚፈሩህ ፡ እኔን ፡ አይተው ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
አቤቱ ፡ ፍርድህ ፡ ጽድቅ ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ ፷፭
በእውነትህም ፡ እንዳስቸገርኸኝ ፡ አወቅሁ ።

የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ሃይማኖትና ሥርዓት

The Ethiopian Orthodox Tewahido Church Faith and Order

www.ethiopianorthodox.org



፸፮ ወበከመ ፡ ነቢብከ ፡ ይኩነኒ ፡ ለገብርከ ።
ይምጽአኒ ፡ ሣህልከ ፡ ወእሕየው ።
፸፯ እስመ ፡ ተመሀርየ ፡ ውእቱ ፡ ሕግከ ።
፸፰ ይትኀፈሩ ፡ ዕቡያን ፡ እስመ ፡ ዐመፃ ፡ መከሩ ፡ ላዕሌየ።
ወአንሰ ፡ እዛዋዕ ፡ በትእዛዝከ ።
፸፱ ይግብኡኒ ፡ እለ ፡ ይፈርሁከ ።
ወእለ ፡ የአምሩ ፡ ስምዐከ ።
፹ ለይኩን ፡ ልብየ ፡ ንጹሐ ፡ በኵነኔከ ፡ ከመ ፡ ኢይትኀፈር

ካፍ ፡ ብሂል ፡ ከሃሊ ፡ እግዚአብሔር ።

፹፩ ካፍ ፡ ኀለፈት ፡ ነፍስየ ፡ ውስተ ፡ አድኅኖትከ ።
ወተወከልኩ ፡ በቃልከ ።
ደክማ ፡ አዕይንትየ ፡ ለመድኀኒትከ ።
፹፪ እንዘ ፡ ይብላ ፡ ማእዜ ፡ ታስተፈሥሐኒ ።
፹፫ እስመ ፡ ኮንኩ ፡ ከመ ፡ ዝቅ ፡ ውስተ ፡ አስሐትያ ።
ወኵነኔከሰ ፡ ኢረሳእኩ ።
፹፬ ሚ ፡ መጠን ፡ እማንቱ ፡ መዋዕሊሁ ፡ ለገብርከ ።
ማእዜ ፡ ትፈትሕ ፡ ሊተ ፡ እምእለ ፡ ይሰዱኒ ።
፹፭ ነገሩኒ ፡ ኃጥኣን ፡ ዛውዐ ።
ወአኮሰ ፡ ከመ ፡ ሕግከ ፡ እግዚኦ ።
፹፮ ኵሉ ፡ ትእዛዝከ ፡ ጽድቅ ።
በዐመፃ ፡ ሰደዱኒ ፡ ርድአኒ ።
፹፯ ሕቀ ፡ ከመ ፡ ዘእምደምሰሱኒ ፡ ውስተ ፡ ምድር ።
ወአንሰ ፡ ኢኀደጕ ፡ ትእዛዘከ ።
፹፰ በከመ ፡ ምሕረትከ ፡ አሕይወኒ ።
ወእዕቀብ ፡ ስምዐ ፡ አፉከ ።

ላሜድ ፡ ብሂል ፡ ልዑል ፡ እግዚአብሔር ።

፹፱ ላሜድ፡እግዚኦ ፡ ለዓለም ፡ ይነብር ፡ ቃልከ ፡
ውስተ ፡ ሰማይ ።
፺ ወለትውልደ ፡ ትውልድ ፡ ጽድቅከ ።
ሣረርካ ፡ ለምድር ፡ ወትነብር ።
ወበትእዛዝከ ፡ ይቀውም ፡ ዕለት ።
፺፩ እስመ ፡ ኵሉ ፡ ቀነይከ ።
፺፪ ሶበ ፡ አኮ ፡ ሕግከ ፡ ተመሀርየ ፡ ውእቱ ።
ትካት ፡ እምተሀጕልኩ ፡ በኀሳርየ ።
ለዓለም ፡ ኢይረስዕ ፡ ኵነኔከ ።
፺፫ እስመ ፡ ቦቱ ፡ አሕየውከኒ ።
፺፬ ዚአከ ፡ አነ ፡ አድኅነኒ ።
እስመ ፡ ኵነኔከ ፡ ኀሠሥኩ ።
፺፭ ኪያየ ፡ ይጸንሑ ፡ ኃጥኣን ፡ ይቅትሉኒ ።
እስመ ፡ ስምዐከ ፡ ለበውኩ ።
፺፮ ለኵሉ ፡ ግብር ፡ ርኢኩ ፡ ማኅለቅቶ ።
ወትእዛዝከሰ ፡ ርሒብ ፡ ፈድፋደ ።

ሜም ፡ ብሂል ፡ ምዑዝ ፡ እግዚአብሔር ።

፺፯ ሜም ፡ጥቀ ፡ አፍቀርኩ ፡ ሕገከ ፡ እግዚኦ ።
ወኵሎ ፡ አሚረ ፡ ተመሀርየ ፡ ውእቱ ።
ወእምጸላእትየ ፡ አጥበበኒ ፡ ትእዛዝከ ።
፺፰ እስመ ፡ ለዓለም ፡ ሊተ ፡ ውእቱ ።
ወእምኵሎሙ ፡ እለ ፡ መሀሩኒ ፡ ጠበብኩ ።
፺፱ እስመ ፡ ተመሀርየ ፡ ውእቱ ፡ ትእዛዝከ ።
ወእምአዕሩግኒ ፡ ጠበብኩ ።
፻ እስመ ፡ ትእዛዘከ ፡ ኀሠሥኩ ።
እምኵሉ ፡ ፍኖተ ፡ ዐመፃ ፡ ከላእኩ ፡ እግርየ ።



ምሕረትህ ፡ ለመጽናናቴ ፡ ትሁነኝ ፡ ፸፮
እንደ ፡ ነገርህም ፡ ለባሪያህ ፡ ይሁነው ።
ሕግህ ፡ ደስታዬ ፡ ናትና ፡ ፸፯
ቸርነትህ ፡ ትምጣልኝ ፡ ሕያውም ፡ እሆናለሁ ።
ትዕቢተኞች ፡ በዓመፅ ፡ ጠመውብኛልና ፡ ይፈሩ ፡ ፸፰
እኔ ፡ ግን ፡ በትእዛዝህ ፡ እጫወታለሁ ።
የሚፈሩህና፡ምስክሮችህን፡የሚያውቁ፡ወደእኔ፡ይመለሱ ፸፱
እንዳላፍር ፡ ልቤ ፡ በሥርዓትህ ፡ የቀና ፡ ይሁን ፡ ፹

ካፍ ፡ ማለት ።

ለእግዚአብሔር የሚሳነው ነገር የሌለ ፤ ሁሉን ማድረግ
የሚቻለው አምላክ ማለት ነው ።

ካፍ ፡ ነፍሴ ፡ ለመድኀኒትህ ፡ ሳሳች ፡ ፹፩
በቃልህም ፡ ታመንሁ ።
መቼ ፡ ታጽናናኛለህ ፡ እያልሁ ፡ ፹፪
ዓይኖቼ ፡ ስለ ፡ ቃልህ ፡ ፈዘዙ ።
በጢስ ፡ እንዳለ ፡ አቁማዳ ፡ ሆኛለሁና ፡ ፹፫
ሥርዓትህን ፡ ግን ፡ አልረሳሁም ።
የባሪያህ ፡ ዘመኖች ፡ ስንት ፡ ናቸው ? ፹፬
በሚያሳድዱኝስ ፡ ላይ ፡ መቼ ፡ ትፈርድልኛለህ ?
ኀጢአተኞች ፡ ጨዋታን ፡ ነገሩኝ ፡ ፹፭
አቤቱ ፡ እንደ ፡ ሕግህ ፡ ግን ፡ አይደለም ።
ትእዛዛትህ ፡ ሁሉ ፡ እውነት ፡ ናቸው ፡ ፹፮
በዓመፅ ፡ አሳደውኛልና ፡ እርዳኝ ።
ከምድር ፡ ሊያጠፉኝ ፡ ጥቂት ፡ ቀርቷቸው ፡ ነበር ፡ ፹፯
እኔ ፡ ግን ፡ ትእዛዛትህን ፡ አልተውሁም ።
እንደ ፡ ምሕረትህ ፡ ሕያው ፡ አድርገኝ ፡ ፹፰
የአፍ ህንም ፡ ምስክር ፡ እጠብቃለሁ ።

ላሜድ ፡ ማለት ።

እግዚአብሔር ፡ ልዑል ባሕርይ የሆነ ማለት ነው ።

ላሜድ ፡ አቤቱ፡ ቃልህ፡ በሰማይ፡ ለዘላለም፡ይኖራል፡ ፹፱
እውነትህ ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ናት ፡ ፺
ምድርን ፡ መሠረትሃት ፡ እርሷም ፡ ትኖራለች ።
ሁሉ ፡ ባሮችህ ፡ ናቸውና ፡ ፺፩
ቀኑ ፡ በትእዛዝህ ፡ ይኖራል ።
ሕግህ ፡ ደስታዬ ፡ ባይሆን ፡ ፺፪
ቀድሞ ፡ በጕስቍልናዬ ፡ በጠፋሁ ፡ ነበር ።
በእርሱ ፡ ሕያው ፡ አድርገኸኛልና ፡ ፺፫
ፍርድህን ፡ ለዘላለም ፡ አልረሳም ።
እኔ ፡ የአንተ ፡ ነኝ፡ ፍርድህን፡ ፈልጌአለሁና፡ አድነኝ ፡ ፺፬
ኀጢአተኞች ፡ ያጠፉኝ ፡ ዘንድ ፡ ጠበቁኝ ፡ ፺፭
ምስክርህን ፡ ግን ፡ መረመርሁ ።
የሥራን ፡ ፍጻሜ ፡ ሁሉ ፡ አየሁ ፡ ፺፮
ትእዛዝህ ፡ ግን ፡ እጅግ ፡ ሰፊ ፡ ነው ።

ሜም ፡ ማለት ።

እግዚአብሔር ፡ ንጹሐ ባሕርይ የሆነ አምላክ ማለት ነው ።

ሜም ፡ አቤቱ፡ ሕግህን ፡ እንደምን ፡ እጅግ፡ ወደድሁ፡ ፺፯
ቀኑን ፡ ሁሉ ፡ እርሱ ፡ ትዝታዬ ፡ ነው ።
ለዘላለም ፡ ለእኔ ፡ ነውና ፡ ፺፰
ትእዛዝህ፡ከጠላቶቼ ፡ ይልቅ ፡ አስተዋይ፡አደረገኝ ።
ምስክርህ ፡ ትዝታዬ ፡ ነውና ፡ ፺፱
ከአስተማሩኝ ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ አስተዋልሁ ።
ትእዛዝህን ፡ ፈልጌአለሁና ፡ ፻
ከሽማግሌች ፡ ይልቅ ፡ አስተዋልሁ ።

፻፩ ክመ ፡ እዕቀብ ፡ ነቢበከ ።
፻፪ ወኢተግሕሥኩ ፡ እምኵነኔከ ።
እስመ ፡ አንተ ፡ ምህርከኒ ።
፻፫ ጥዑም ፡ ለጕርዔየ ፡ ነቢብከ ።
እመዓር ፡ ወሦከር ፡ ጥዕመኒ ፡ ለአፉየ ።
፻፬ ወእምትእዛዝከ ፡ ለበውኩ ።
በእንተዝ ፡ ሰላ ፡ ፍኖተ ፡ ዐመፃ ፡ ጸላእኩ ።

ኖን ፡ ብሂል ፡ ንትሉ ፡ እግዚአብሔር ።

፻፭ ኖን ፡ ማኅቶት ፡ ለእግርየ ፡ ሕግከ ።
ብርሃን ፡ ለፍኖትየ ።
፻፮ መሐልኩ ፡ ወአጥባዕኩ ፡ ከመ ፡ እዕቀብ ፡
ኵነኔ ፡ ጽድቅከ ።
፻፯ ወሐመምኩ ፡ ፈድፋደ ።
እግዚኦ ፡ አሕይወኒ ፡ በከመ ፡ ነቢብከ ።
፻፰ ሥመር ፡ እግዚኦ ፡ ቃለ ፡ አፉየ ።
ወምህረኒ ፡ ኵነኔከ ።
፻፱ ነፍስየ ፡ ውስተ ፡ እዴከ ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ።
ወኢረሳዕኩ ፡ ሕገከ ።
፻፲ ሠርዑ ፡ ሊተ ፡ ኃጥኣን ፡ መሥገርተ ።
ወኢስሕትኩ ፡ እምትእዛዝከ ።
ወወረስኩ ፡ ስምዐከ ፡ ለዓለም ።
፻፲፩ እስመ ፡ ሐሤቱ ፡ ለልብየ ፡ ውእቱ ።
ሜጥኩ ፡ ልብየ ፡ ከመ ፡ እግበር ፡ ትእዛዘከ ።
፻፲፪ ለዓለም ፡ ዘእንበለ ፡ ሒስ ።

ሳምኬት ፡ ብሂል ፡ ሰፉኒ ፡ እግዚአብሔር ።

፻፲፫ ሳምኬት ፡ ዐማፅያነ ፡ ጸላእኩ ፡ ሕገከሰ ፡ አፍቀርኩ ።
፻፲፬ ረዳኢየ ፡ ወምስካይየ ፡ አንተ ።
ወበቃልከ ፡ ተወከልኩ ።
፻፲፭ ተገሐሡ ፡ እምኔየ ፡ ዐማፅያን ።
ወእኅሥሥ ፡ ትእዛዘ ፡ ለአምላኪየ ።
፻፲፮ ተወከፈኒ ፡ በከመ ፡ ነቢብከ ፡ ወአሕየው ።
ወኢታስተኀፍረኒ ፡ እምተስፋየ ።
፻፲፯ ርድአኒ ፡ ወአድኅነኒ ።
ወአነብብ ፡ ኵነኔከ ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ።
አኅሰርኮሙ ፡ ለኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይርኅቁ ፡ እምትእዛዝከ ።
፻፲፰ እስመ ፡ ዐመፃ ፡ ፍትወቶሙ ።
፻፲፱ ዐላውያን ፡ እሙንቱ ፡ ኵሎሙ ፡ ኃጥኣነ ፡ ምድር ።
በእንተዝ ፡ አፍቀርኩ ፡ ስምዐከ ።
፻፳ አውድድ ፡ ውስተ ፡ ሥጋየ ፡ ፈሪሆተከ ።
እስመ ፡ ፈራህኩ ፡ እምኵነኔከ ።

ዔ ፡ ብሂል ፡ ዐቢይ ፡ እግዚአብሔር ።

፻፳፩ ዔ ፡ ገበርኩ ፡ ፍትሐ ፡ ወጽድቀ ።
ኢትመጥወኒ ፡ ለእለ ፡ ይሣቅዩኒ ።
፻፳፪ ጽንሖ ፡ ለገብርከ ፡ ውስተ ፡ ሠናይ ።
ወኢይትዐገሉኒ ፡ ዕቡያን ።
፻፳፫ ደከማ ፡ አዕይንትየ ፡ ለአድኅኖትከ ፡ ወለቃለ ፡ ጽድቅከ ።
፻፳፬ ግበር ፡ ለገብርከ ፡ በከመ ፡ ምሕረትከ ።
ወምህረኒ ፡ ኵነኔከ ።
፻፳፭ ገብርከ ፡ አነ ፡ አለብወኒ ።
ወአእምር ፡ ስምዐከ ።
፻፳፮ ጊዜ ፡ ገቢር ፡ ለእግዚአብሔር ።
ወዐለዉ ፡ ሕገከ ።
በእንተዝ ፡ አፍቀርኩ ፡ ትእዛዘከ ።
፻፳፯ እምወርቅ ፡ ወእምጳዝዮን ።
፻፳፰ በእንተዝ ፡ አርታዕኩ ፡ ኀበ ፡ ኵሉ ፡ ትእዛዝከ ።
ኵሎ ፡ ፍኖተ ፡ ዐመፃ ፡ ጸላእኩ ።



ነገርህን ፡ እጠብቅ ፡ ዘንድ ፡ ፻፩
ከክፉ ፡ መንገድ ፡ ሁሉ ፡ እግሬን ፡ ከለከልሁ ።
አስተምረኸኛልና ፡ ከፍርድህ ፡ አልራቅሁም ። ፻፪
ነገርህ ፡ ለጕረሮዬ ፡ ጣፋጭ ፡ ነው ፡ ፻፫
ከማርና ፡ ከወለላ ፡ ይልቅ ፡ ለአፌ ፡ ጣፋጠኝ ።
ከትእዛዝህ ፡ የተነሣ ፡ አስተዋልሁ ፡ ፻፬
ስለዚህ ፡ የሐሰትን ፡ መንገድ ፡ ጠላሁ ።

ኖን ፡ ማለት ።
እግዚአብሔር ፡ የነገሥታት ንጉሥ የገዥዎች ገዥ
የሆነ አምላክ ማለት ነው ።

ኖን ፡ ሕግህ ፡ ለእግሬ ፡ መብራት ፡ ፻፭
ለመንገዴ ፡ ብርሃን ፡ ነው ።
የጽድቅህን፡ፍርድ፡እጠብቅ፡ዘንድ፡ማልሁ፡አጸናሁም። ፻፮
እጅግ ተቸገርሁ አቤቱ እንደ ነገርህ ሕያው አድርገኝ። ፻፯
አቤቱ ፡ የአፌን ፡ ነገር ፡ ተቀበል ፡ ፻፰
ፍርድህንም ፡ አስተምረኝ ።
ነፍሴ ፡ ሁልጊዜ ፡ በእጅህ ፡ ውስጥ ፡ ናት ፡ ፻፱
ሕግህን ፡ ግን ፡ አልረሳሁም ።
ኀጢአተኞች ፡ ወጥመድን ፡ ዘረጉብኝ ፡ ፻፲
ከትእዛዝህ ፡ ግን ፡ አልወጣሁም ።
የልቤ ፡ ደስታ ፡ ነውና ፡ ፻፲፩
ምስክርህን ፡ ለዘላለም ፡ ወረስሁ ።
ለዘላለም ፡ ለፍጻሜውም ፡ ፻፲፪
ትእዛዝህን፡አደርግ ፡ ዘንድ፡ ልቤን ፡ አዘነበልሁ ።

ሳምኬት ፡ ማለት ።
እግዚአብሔር ሁሉን የሚገዛ አምላክ ማለት ነው ።

ሳምኬት፡ ዐመፀኞችን፡ጠላሁ፡ሕግህን፡ግን፡ወደድሁ። ፻፲፫
አንተ ፡ረዳቴና ፡ መጠጊያዬ ፡ ነህ ፡ ፻፲፬
በቃልህም ፡ ታመንሁ ።

እናንተ ፡ ኃጢአኞች ፡ ከእኔ ፡ ራቁ ፡ ፻፲፭
የአምላኬንም ፡ ትእዛዝ ፡ ልፈልግ ።
እንደ ፡ ነገርህ ፡ ደግፈኝ ፡ ሕያውም ፡ እሆናለሁ ፡ ፻፲፮
ከተስፋዬም ፡ አልፈር ።
እርዳኝ ፡ እድናለሁም ፤ ፻፲፯
ሁል ፡ ጊዜም ፡ ሥርዓትህን ፡ እመረምራለሁ ።
ምኞታቸው ፡ ዓመፃ ፡ ነውና ፡ ፻፲፰
ከሥርዓትህ ፡ የሚርቁትን፡ ሁሉ ፡ አጕሳቆልኻቸው ።
የምድርን ኀጢአተኞች ሁሉ እንደ ርኵሰት አጥፋቸው ። ፻፲፱
ስለዚህ ፡ ምስክርህን ፡ ወደድሁ ።
ሥጋዬ ፡ አንተን ፡ ከመፍራት ፡ የተነሣ ፡ ደነገጠ ፤ ፻፳
ከፍርድህ ፡ የተነሣ ፡ ፈርቻለሁና ።

ዔ ፡ ማለት ።
እግዚአብሔር ታላቅና ገናና የሆነ አምላክ ማለት ነው ።

ዔ ፤ ፍርድንና ፡ ጽድቅን ፡ ሠራሁ ፤ ፻፳፩
ለሚያስጨንቁኝ ፡ አሳልፈህ ፡ አትስጠኝ ።
ባሪያህን ፡ በመልካም ፡ ጠብቀው ፤ ፻፳፪
ትዕቢተኞችም ፡ አይጋፉኝ ።
ዓይኖቼ ፡ ለማዳንህ ፡ ፻፳፫
ለጽድቅህም ፡ ቃል ፡ ፈዘዙ ።
ለባሪያህ ፡ እንደ ፡ ምሕረትህ ፡ አድርግ ፡ ፻፳፬
ሥርዓትህንም ፡ አስተምረኝ ።
እኔ፡ባሪያህ ፡ ነኝ ፡ እንዳስተውል ፡ አድርገኝ ፡ ፻፳፭
ምስክርህንም ፡ አውቃለሁ ።
ለእግዚአብሔር ፡ የሥራ ፡ ጊዜ ፡ አለው ፡ ፻፳፮
ሕግህንም ፡ሻሩት ።
ከወርቅና ፡ ከዕንቍ ፡ ይልቅ፡ትእዛዝህን፡ወደድሁ ፤ ፻፳፯
ስለዚህ ፡ ወደ ፡ ትእዛዝህ ፡ ሁሉ ፡ አቀናሁ ፡ ፻፳፰
የዓመፅንም ፡ መንገድ ፡ ሁሉ ፡ ጠላሁ ።

ፌ ፡ ብሂል ፡ ፍትው ፡ እግዚአብሔር ።

፻፳፱ ፌ ፡ መንክር ፡ ስምዕከ ።
በእንተዝ ፡ ኀሠሠቶ ፡ ነፍስየ ።
፻፴ ነገረ ፡ ቃልከ ፡ ያበርህ ፡ ወያጠብብ ፡ሕፃናተ ።
፻፴፩ አፉየ ፡ ከሠትኩ ፡ ወነፍስየ ፡ አናኅኩ ።
እስመ ፡ ትእዛዘከ ፡ እፈቅርኩ ።
ነጽር ፡ ላዕሌየ ፡ ወተሣሀለኒ ።
፻፴፪ በከመ ፡ ፍትሖሙ ፡ ለእለ ፡ ያፈቅሩ ፡ ስመ ከ ።
፻፴፫ አርትዕ ፡ ፍኖትየ ፡ ወሑረትየ ፡ በከመ ፡ ነቢብከ ።
ወኢይምዐኒ ፡ ኵሉ ፡ ኃጢአት ።
፻፴፬ አድኅነኒ ፡ እምትዕግልተ ፡ዕጓለ ፡ እመሕያው ።
ወእዕቀብ ፡ ትእዛዘከ ።
፻፴፭ አብርህ ፡ ገጸከ ፡ ላዕለ ፡ ገብርከ ።
ወምህረኒ ፡ ኵነኔከ ።
ሙኃዘ ፡ ማይ ፡ ወረደ ፡ እምአዕይንትየ
፻፴፮ ወእመ ፡ አኮሰ ፡ እምኢዐቀብኩ ፡ ሕገከ ።

ጻዴ ፡ ብሂል ፡ ጻድቅ ፡ እግዚአብሔር ።

፻፴፯ ጻዴ ፡ ጻድቅ ፡ አንተ ፡ እግዚኦ፡ወርቱዕ ፡ ኵሉ፡ኵነኔከ ።
፻፴፰ ወአዘዝከ ፡ ስምዐከ ፡ በጽድቅ ።
ወርቱዕ ፡ ፈድፋደ ።
መስወኒ ፡ ቅንዓተ ፡ ቤትከ ።
፻፴፱ እስመ ፡ ረስዑ ፡ ትእዛዘከ ፡ ጸላእትየ ።
፻፵ ርሱን ፡ ቃልከ ፡ ፈድፋደ ። ወገብርከሰ ፡ አፍቀሮ ።
፻፵፩ ወሬዛ ፡ አነ ፡ ወትሑት ።
ሕገከሰ ፡ ኢረሳዕኩ ።

፻፵፪ ጽድቅከሰ ፡ ጽድቅ ፡ ዘለዓለም ።
ወቃልከኒ ፡ እሙን ፡ ውእቱ ።
፻፵፫ ሕማም ፡ ወምንዳቤ ፡ ረከበኒ ።
ወትእዛዝከሰ ፡ ተመሐርየ ፡ ውእቱ ።
፻፵፬ ጽድቅ ፡ ውእቱ ፡ ስምዕከ ፡ ለዓለም ።
አለብወኒ ፡ ወአሕይወኒ ።

ቆፍ ፡ ብሂል ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ።

፻፵፭ ቆፍ ፡ ጸራኅኩ ፡ በኵሉ ፡ ልብየ ፡ ስምዐኒ ፡ እግዚእ ።
ወኀሠሥኩ ፡ ኵነኔከ ።
፻፵፮ ጸራኅኩ ፡ ኀቤከ ፡ ስምዐኒ ፡ ወአድኅነኒ ።
ወእዕቀብ ፡ ስምዐከ ።
፻፵፯ በጸሕኩ ፡ ማዕከለ ፡ አድባር ፡ ወከላሕኩ ።
እስመ ፡ ቃለከ ፡ ተሰፈውኩ ።
በጽሐ ፡ አዕይንትየ ፡ ለገይሥ ።
፻፵፰ ከመ ፡ እንብብ ፡ ቃለከ ።
ስማዕ ፡ እግዚእ ፡ ቃልየ ፡ በከመ ፡ ሣህልከ ።
፻፵፱ ወአሕይወኒ ፡ በከመ ፡ ፍትሕከ ።
፻፶ ቀርቡ ፡ እለ ፡ ሮዱኒ ፡ በዐመፃ ።
ወእምሕግከሰ ፡ ርኁቁ ።
፻፶፩ ቅሩብ ፡ አንተ ፡ እግዚእ ፤ ወርቱዕ ፡ ኵሉ ፡ ፍናዊከ ።
እምትካት ፡ አእመርኩ ፡ስ ምዐከ ።
፻፶፪ ከመ ፡ ለዓለም ፡ ሣረርኮን ።

ሬስ ፡ ብሂል ፡ ርዑስ ፡ እግዚአብሔር ።

ሬስ ፡ ርኢ ፡ ሕማምየ ፡ ወአድኅነኒ ።
፻፶፫ እስመ ፡ ኢረሳእኩ ፡ ሕገከ ።
፻፶፬ ፍታሕ ፡ ፍትሕየ ፡ ወባልሐኒ ።
ወበእንተ ፡ ቃልከ ፡ አሕይወኒ ።



ፌ ፡ ማለት ።

እግዚአብሔር ፡ ተወዳጅ የሆነ አምላክ ማለት ነው ።

ፌ ፡ ምስክሮችህ ፡ ድንቆች ፡ ናቸው ፡ ፻፳፱
ስለዚህ ፡ ነፍሴ ፡ ፈለገቻቸው ።
የቃልህ ፡ ፍቹ ፡ ያበራል ፡ ፻፴
የዋሃንንም ፡ አስተዋዮች ፡ ያደርጋል ።
አፌን ፡ ከፈትሁ ፡ አልከለከልሁም ፤ ፻፴፩
ወደ ፡ ትእዛዝህ ፡ ናፍቄአለሁና ።
ስምህን ፡ ለሚወዱ ፡ እንደምታደርገው ፡ ፍርድ ፡ ፻፴፪
ወደ ፡ እኔ ፡ ተመልከት ፡ ማረኝም ።
አካሄዴን ፡ እንደ ፡ ነገርህ ፡ አቅና ፤ ፻፴፫
ኀጢአትም ፡ ሁሉ ፡ አይግዛኝ ።
ከሰው ፡ ግፍ ፡ አድነኝ ፡ ፻፴፬
ትእዛዝህንም ፡ እጠብቃለሁ ።
በባሪያህ ፡ ላይ ፡ ፊትህን ፡ አብራ ፡ ፻፴፭
ሥርዓትህንም ፡ አስተምረኝ ።
ሕግህን ፡ አልጠበቅሁምና ፡ ፻፴፮
የውኃ ፡ ፈሳሽ ፡ ከዓይኖቼ ፡ ፈሰሰ ።

ጻዴ ፡ ማለት ።

እግዚአብሔር ፡ ሐሰት የሌለበት ዕውነተኛ አምላክ ማለት ነው ።

ጻዴ ፡ አቤቱ፡አንተ፡ጻድቅ፡ነህ፡ፍርድህም፡ቅን፡ነው ፡ ፻፴፯
ምስክርህን ፡ በጽድቅ ፡ አዘዝህ ፡ ፻፴፰
እጅግም ፡ ቅን ፡ ነው ።
ጠላቶቼ ፡ ትእዛዝህን ፡ ረስተዋልና ፡ ፻፴፱
የቤትህ ፡ ቅናት ፡ አቀለጠኝ ።
ቃልህ ፡ እጅግ ፡ የነጠረ ፡ ነው ፡ ፻፵
ባሪያህም ፡ ወደደው ።
እኔ ፡ ታናሽና ፡ የተናቅሁ ፡ ነኝ ፡ ፻፵፩
ትእዛዛትህን ፡ ግን ፡ አልረሳሁም ።

ጽድቅህ ፡ የዘላለም ፡ ጽድቅ ፡ ነው ። ፻፵፪
ቃልህም ፡ እውነት ፡ ነው ።
መከራና ፡ ችግር ፡ አገኙኝ ፡ ፻፵፫
ትእዛዛትህ፡ ግን ፡ ደስታዬ ፡ ናቸው ።
ምስክርህ ፡ ለዘላለም ፡ ጽድቅ ፡ ነው ። ፻፵፬
እንዳስተውል ፡ አድርገኝ ፤ አድነኝም ።

ቆፍ ፡ ማለት ።

እግዚአብሔር ፡ [illegible]

ቆፍ ፡ በፍጹም ፡ ልቤ ፡ ጮኽሁ ፡ አቤቱ ፡ ስማኝ ፡ ፻፵፭
ሥርዓትህን ፡ እፈልጋለሁ ።
ወደ ፡ አንተ ፡ ጮኽሁ ፡ አድነኝ ፡ ፻፵፮
ምስክርህንም ፡ እጠብቃለሁ ።
ማለዳ ፡ ጮኽሁ ፡ ፻፵፯
ነገርህንም ፡ ተስፋ ፡ አድርጌአለሁ ።
ነገርህን ፡ አስብ ፡ ዘንድ ፡ ፻፵፰
ዓይኖቼ ፡ ለመማለድ ፡ ቀደሙ ።
አቤቱ ፡ እንደ ፡ ቸርነትህ ፡ ድምፄን ፡ ስማ ፡ ፻፵፱
እንደ ፡ ፍርድህ ፡ ሕያው ፡ አድርገኝ ።
በዓመፃ ፡ የሚያሳድዱኝ ፡ ቀረቡ ፡ ፻፶
ከሕግህም ፡ ራቁ ።
አቤቱ ፡ አንተ ፡ ቅርብ ፡ ነህ ፡ ፻፶፩
መንገዶችህም ፡ ሁሉ ፡ ቅኖች ፡ ናቸው ።
ከዘለዓለም ፡ እንደ ፡ መሠረትኸው ፡ ፻፶፪
ከቀድሞ ፡ ጀምሮ ፡ ከምስክርህ ፡ የተነሣ ፡ አወቅሁ ።

ሬስ ፡ ማለት ።

እግዚአብሔር ፡ [illegible]

ሬስ ፡ ሕግህን ፡ አልረሳሁምና ፡ ፻፶፫
ችግሬን ፡ ተመልከት ፡ አድነኝም ።
ፍርዴን ፡ ፍረድ ፡ አድነኝም ፡ ፻፶፬
ስለ ፡ ቃልህ ፡ ሕያው ፡ አድርገኝ ።

፻፶፭ ርኁቅ ፡ ሕይወት ፡ እምኃጥአን ።
እስመ ፡ ኢኀሠሡ ፡ ኵነኔከ ።
፻፶፮ ብዙኅ ፡ ሣህልከ ፡ እግዚኦ ፡ ፈድፋደ ።
ወአሕይወኒ ፡ በከመ ፡ ፍትሕከ ።
፻፶፯ ብዙኃን ፡ እለ ፡ ሮዱኒ ፡ ወአመንደቡኒ ።
ወኢተግሕሥኩ ፡ እምስምዕከ ።
ርኢኩ ፡ አብዳነ ፡ ወተከዘኩ ።
፻፶፰ እስመ ፡ ኢዐቀቡ ፡ ቃለከ ።
፻፶፱ ርኢ ፡ ከመ ፡ አፍቀርኩ ፡ ትእዛዘከ ።
እግዚኦ ፡ አሕይወኒ ፡ በሣህልከ ።
፻፷ ቀዳሚ ፡ ቃልከ ፡ ጽድቅ ፡ ውእቱ ።
ወለዓለም ፡ ኵሉ ፡ ኵነኔከ ፡ ጽድቅ ።

ሳን ፡ ብሂል ፡ ሰብሕ ፡ እግዚአብሔር ።

፻፷፩ ሳን ፡ መላእክት ፡ ሰደዱኒ ፡ በከንቱ ።
ወእምቃልከ ፡ ደንገጸኒ ፡ ልብየ ።
ወበቃልከ ፡ ተፈሣሕኩ ።
፻፷፪ ከመ ፡ ዘረከበ ፡ ምህርካ ፡ ብዙኀ ።
፻፷፫ ዐመፃ ፡ ጸላእኩ ፡ ወአስቈረርኩ ።
ወሕገከሰ ፡ አፍቀርኩ ።
ስብዐ ፡ ለዕለትየ ፡ እሴብሐከ ።
፻፷፬ በእንተ ፡ ኵነኔ ፡ ጽድቅከ ።
፻፷፭ ሰላም ፡ ብዙኅ ፡ ለእለ ፡ ያፈቅሩ ፡ ስመከ ።
ወአልቦሙ ፡ ዕቅፍት ።
፻፷፮ ተሰፈውኩ ፡ አድኅኖተከ ፡ እግዚኦ ።
ወዐቀብኩ ፡ ትእዛዘከ ።
፻፷፯ ዐቀበት ፡ ነፍስየ ፡ ስምዐከ ።
ወአፍቀረቶ ፡ ፈድፋደ ።
ዐቀብኩ ፡ ትእዛዘከ ፡ ወስምዐከኒ ።
፻፷፰ እስመ ፡ ኵሉ ፡ ፍናውየ ፡ ቅድሜከ ፡ እግዚኦ ።

ታው ፡ ብሂል ፡ ትጉህ ፡ እግዚአብሔር ።

፻፷፱ ታው ፡ ለትቅረብ ፡ ስእለትየ ፡ ኀቤከ ፡ እግዚኦ ።
ወበከመ ፡ ቃልከ ፡ አለብወኒ ።
፻፸ ትብጻሕ ፡ አስተብቍዖትየ ፡ ቅድሜከ ፡ እግዚኦ ።
ወበከመ ፡ ቃልከ ፡ አድኅነኒ ።
ጕሥዓ ፡ ከናፍርየ ፡ ስብሐቲከ ።
፻፸፩ እስመ ፡ ምህርከኒ ፡ ኵነኔከ ። ነበበ ፡ ልሳንየ ፡ ቃለከ ።
፻፸፪ እስመ ፡ ጽድቅ ፡ ኵሉ ፡ ትእዛዝከ ።
ይኩነኒ ፡ የማንከ ፡ ከመ ፡ ያድኅነኒ ።
፻፸፫ እስመ ፡ ትእዛዘከ ፡ አፍቀርኩ ።
፻፸፬ አፍቀርኩ ፡ አድኅኖተከ ፡ እግዚኦ ።
ወሕግከሰ ፡ ተመሀርየ ፡ ውእቱ ።
፻፸፭ ትሕየወኒ ነፍስየ ወእሰብሕከ፤ወይርድአኒ ኵነኔ ዚአከ።
፻፸፮ ተረሳእኩ ፡ ከመ ፡ በግዕ ፡ ዘተገድፈ ።
ኅሥሥ ፡ ለገብርከ ፡ እስመ ፡ ትእዛዘከ ፡ ኢረሳእኩ ።

መዝሙር ፡ ፻፲፱ ።

በእንተ ጢስ ።

፩ ኀቤከ ፡ እግዚኦ ፡ ጸራሕኩ ፡ ሶበ ፡ ተመንደብኩ ፡ ወሰማዕከኒ ።
፪ እግዚኦ ፡ አድኅና ፡ ለነፍስየ ፡ እምከናፍረ ፡ ዐመፃ ።
፫ ወእምልሳን ፡ ጽልሑት ።
ምንተ ይሁቡከ ወምንተ ይዌስኩከ በእንተ ከናፍረ ጕሕሉት።
አሕፃሁ ፡ ለኀያል ፡ ስሑል ።
፬ ከመ ፡ አፍሐመ ፡ ሐቅል ።
፭ ሰይ ፡ ልየ ፡ ዘርኅቀ ፡ ማኅደርየ ።
ወኀደርኩ ፡ ውስተ ፡ አዕጻዳት ፡ እለ ፡ ቄዳር ።
ብዙኀ ፡ ተዐገሠት ፡ ነፍስየ ።



መድኃኒት ፡ ከኃጥአን ፡ ሩቅ ፡ ነው ፡ ፻፶፭
ሥርዓትህን ፡ አልፈለጉምና ፡
አቤቱ ፡ ቸርነትህ ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ነው ፡ ፻፶፮
እንደ ፡ ፍርድህ ፡ ሕያው ፡ አድርገኝ ።
የአሳደዱኝና ፡ የአስጨነቁኝ ፡ ብዙዎች ፡ ናቸው ፤ ፻፶፯
ከምስክርህ ፡ ግን ፡ ፈቀቅ ፡ አላልሁም ።
ቃልህን ፡ አልጠበቁምና ፡ ፻፶፰
ግብዞችን ፡ አይቼ ፡ አዘንሁ ።
ትእዛዝህን ፡ እንደ፡ ወደድሁ ፡ ተመልከት ፡ ፻፶፱
አቤቱ ፡ በምሕረትህ ፡ ሕያው ፡ አድርገኝ ።
የቃልህ ፡ መጀመሪያ ፡ እውነት ፡ ነው ፡ ፻፷
የጽድቅህም ፡ ፍርድ ፡ ሁሉ ፡ ለዘላለም ፡ ነው ።

ሳን ፡ ማለት ።

እግዚአብሔር ፡ በሥራው ፡ ሁሉ ፡ የተመሰገነ ፡ ማለት ፡ ነው ።

ሳን ፡ ገዥዎች ፡ በከንቱ ፡ አሳደዱኝ ፡ ፻፷፩
ከቃልህ ፡ የተነሣ ፡ ግን ፡ ልቤ ፡ ደነገጠብኝ ።
ብዙ ፡ ምርኮ ፡ እንደ ፡ አገኘ ፡ በነገርህ ፡ ደስ ፡ አለኝ ፡ ፻፷፪
ዓመፃን ፡ ጠላሁ ፡ ተጸየፍሁም ፡ ፻፷፫
ሕግህን ፡ ግን ፡ ወደድሁ ።
ስለ፡ጽድቅህ፡ፍርድ፡ሰባት፡ጊዜ፡በቀን፡አመሰግንሃለሁ ፻፷፬
ሕግህን ፡ ለሚወዱ ፡ ብዙ ፡ ሰላም ፡ ነው ፡ ፻፷፭
እንቅፋትም ፡ የለባቸውም ።
አቤቱ ፡ ማዳንህን ፡ ተስፋ ፡ አደረግሁ ፡ ፻፷፮
ትእዛዛትህንም ፡ ጠበቅሁ ።
ነፍሴ ፡ ምስክርህን ፡ ጠበቀች ፡ ፻፷፯
እጅግም ፡ ወደደችው ።
መንገዶቼ ፡ ሁሉ ፡ በፊትህ ፡ ናቸውና ፡ ፻፷፰
ትእዛዝህንና ፡ ምስክርህን ፡ ጠበቅሁ ።

ታው ፡ ማለት ።

እግዚአብሔር ፡ ስንቅልፍ ፡ የሌለበት ፡ ትጉህ ፤ ድካም ፡ የማይሰማው ፡ [illegible] ፡ ማለት ፡ ነው ።

ታው ፡ አቤቱ ፡ ጸሎቴ ፡ ወደ ፡ ፊትህ፡ትቅረብ ፡ ፻፷፱
እንደ ፡ ቃልህም ፡ አስተዋይ ፡ አድርገኝ ።
ልመናዬ ፡ ወደ ፡ ፊትህ ፡ ትድረስ ፡ ፻፸
እንደ ፡ ቃልህ ፡ አድነኝ ።
ሥርዓትህን ፡ አስተምረኸኛልና ፡ ፻፸፩
ከንፈሮቼ ፡ ምስጋናን ፡ አወጡ ።
ትእዛዛትህ ፡ ሁሉ ፡ ጽድቅ ፡ ናቸውና ፡ ፻፸፪
አንደበቴ ፡ ቃልህን ፡ ተናገረ ።
ትእዛዛትህን ፡ መርጫለሁና ፡ ፻፸፫
እጅህ ፡ የሚያድነኝ ፡ ይሁን ።
አቤቱ ፡ ማዳንህን ፡ ናፈቅሁ ፡ ፻፸፬
ሕግህም ፡ ደስታየ ፡ ነው ።
ነፍሴ ፡ ትኑርልኝ ፡ ታመሰግንህማለች ፡ ፻፸፭
ፍርድህም ፡ ይርዳኝ ።
እንደ ፡ ተጣለ ፡ በግ ፡ ጠፋሁ ፡ ፻፸፮
ትእዛዛትህን ፡ አልረሳሁምና ፡ ባሪያህን ፡ ፈልገው ።

መዝሙር ፡ ፻፲፱ ።

ስለ ፡ ራሱ ።

ስለ ተጨነቅሁ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኽሁ ፡ ሰማኝም ። ፩
ከዓመፀኛ ፡ ከንፈር ፡ ከሸንጋይም ፡ አንደበት ፡ አቤቱ ፡ ነፍሴን ፡ አድናት። ፪
ስለ ፡ ሸንጋላ ፡ አንደበት ፡ ምን ፡ ይሰጡሃል ። ምንስ ፡ ይጨምሩልሃል ። ፫
እንደ ፡ በረሃ ፡ ዕንጨት ፡ ፍም ፡ የኃይለኞች ፡ ፍላጻች ፡ የተሳሉ ፡ ናቸው ። ፬
መኖሪያዬ ፡ የራቀ ፡ እኔ ፡ ወዮልኝ ፡ ፭
በቄዳር ፡ ድንኳኖች ፡ አደርሁ ።

፮ ምስለ ፡ እለ ፡ ይጸልኡ ፡ ሰላመ ።
፯ እንዘ ፡ ሰላማዊ ፡ አነ ።
ሶበ ፡ እትናገሮሙ ፡ ይጸብኡኒ ፡ በከንቱ ።

መዝሙር ፡ ፻፳ ።

በእንተ ትሩፋን ።

፩ አንሣእኩ ፡ አዕይንትየ ፡ መንገለ ፡ አድባር ።
እምአይቴ ፡ ይምጻእ ፡ ረድኤትየ ።
፪ ረድኤትየሰ ፡ እምኀበ ፡ እግዚአብሔር ።
ዘገብረ ፡ ሰማየ ፡ ወምድረ ።
፫ ወኢይሁብን ፡ ሁከተ ፡ ለእገርየ ።
ወኢይዴቅስ ፡ ዘየዐቅበከ ።
፬ ናሁ፡ኢይዴቅስ፡ወኢይነውም፡ዘየዐቅቦ፡ለእስራኤል ።
፭ እግዚአብሔር ፡ ይዕቀብከ ፤ ወእግዚአብሔር ፡ ይከድንከ ፡ በየማነ ፡ እዴሁ ።
፮ መዓልተ ፡ ፀሐይ ፡ ኢያውዒከ ።
ወኢወርኅ ፡ በሌሊት ።
፯ እግዚአብሔር ፡ ይዕቀብከ ፡ እምኵሉ ፡ እኩይ ።
ወይትማሐፀና ፡ ለነፍስከ ፡ እግዚአብሔር ።
እግዚአብሔር ፡ ይዕቀብከ፡በንግደትከ፡ወበእትወትከ፤
፰ እምይእዜ ፡ ወእስከ ፡ ለዓለም ።

መዝሙር ፡ ፻፳፩ ።

በእንተ ትሩፋን ።

፩ ተፈሣሕኩ ፡ እስመ ፡ ይቤሉኒ ፡ ቤተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነሐውር ።
፪ ወቆማ ፡ እገሪነ ፡ ውስተ ፡ አዕጻድኪ ፡ ኢየሩሳሌም ።
፫ ኢየሩሳሌምሰ ፡ ሕንጽት ፡ ከመ ፡ ሀገር ፡
እለ ፡ ከማሃ ፡ ወኅቡረ ፡ ምስሌሃ ።
እስመ ፡ ህየ ፡ ዐርጉ ፡ አሕዛብ ።
ሕዝበ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሰምዐ ፡ እስራኤል ።
፬ ከመ ፡ ይግነዩ ፡ ለስምከ ፡ እግዚኦ ።
፭ እስመ ፡ ህየ ፡ አንበሩ ፡ መናብርቲሆሙ ፡ ለኰንኖ ።
መናብርተ ፡ ቤተ ፡ ዳዊት ።
፮ ወተዝያነዉ ፡ ዳኅናሃ ፡ ለኢየሩሳሌም ።
ወፍሥሐሆሙ ፡ ለእለ ፡ ያፈቅሩ ፡ ስመከ ።
፯ ይኩን ፡ ሰላም ፡ በኀይልኪ ።
ወትፍሥሕት ፡ ውስተ ፡ ማኅፈደ ፡ ክበዲከ ።
፰ በእንተ ፡ አኀውየ ፡ ወቢጽየ ።
ይትናገሩ ፡ ሰላመ ፡ በእንቲአኪ ።
፱ ወበእንተ ፡ ቤተ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላኪየ ፡ ኀሠሥኩ ፡ ሠናይተኪ ።

መዝሙር ፡ ፻፳፪ ።

በእንተ ትሩፋን ።

፩ ኀቤከ ፡ እግዚኦ ፡ አንቃዕዶነ ፡ አዕይንቲነ ፡ ዘትነብር ውስተ ፡ ሰማይ ።
፪ ናሁ ፡ ከመ ፡ አዕይንተ ፡ አግብርት ፡ ውስተ ፡ እደ ፡ አጋዕዝቲሆሙ ።
ወከመ ፡ ዐይነ ፡ አመት ፡ ውስተ ፡ እደ ፡ እግዝእታ ።
ከማሁ ፡ አዕይንቲነ ፡ ኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክነ።
እስከ ፡ አመ ፡ ይሣሀለነ ።
፫ ተሣሀለነ ፡ እግዚኦ ፡ ተሣሀለነ ።
እስመ ፡ ፈድፋደ ፡ ጸገብነ ፡ ጽዕለተ ።
ወፈድፋደ ፡ ጸግበት ፡ ነፍስነ ።
፬ ጽዕለተ ፡ ብዑላን ፡ ወኀሳረ ፡ ዕቡያን ።



ሰላምን ፡ ከሚጠሉ ፡ ጋራ ፡ ፮
ነፍሴ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ኖረች ።
እኔ ፡ ሰላማዊ ፡ ነኝ ፡ ፯
በተናገርኋቸው ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ በከንቱ ፡ ተሰለፉብኝ ።

መዝሙር ፡ ፻፳፩ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

ዓይኖቼን ፡ ወደ ፡ ተራሮች ፡ አነሣሁ ፡ ፩
ረዳቴ ፡ ከወዴት ፡ ይምጣ ?
ረዳቴ ሰማይና ምድርን ከሠራ ከእግዚአብሔር ዘንድ ነው ። ፪
እግሮችህን ፡ ለመናወጥ ፡ አይሰጣቸውም ፡ ፫
የሚጠብቅህም ፡ አይተኛም ።
እነሆ ፡ እስራኤልን ፡ የሚጠብቅ ፡ አይተኛም ፡
አያንቀላፋምም ። ፬
እግዚአብሔር ፡ ይጠብቅሃል ፡ ፭
እግዚአብሔር ፡ በቀኝ ፡ እጅህ ፡ በኩል፡ ይጋርድሃል ።
ፀሐይ ፡ በቀን ፡ አያቃጥልህም ፡ ጨረቃም ፡ በሌሊት ፡ ፮
እግዚአብሔር ፡ ከክፉ ፡ ሁሉ ፡ ይጠብቅሃል ፡ ፯
ነፍስህንም ፡ ይጠብቃታል ።
ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ፰
እግዚአብሔር፡መውጣትህንና፡መግባትህን፡ይጠብቃል ።

መዝሙር ፡ ፻፳፪ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

ወደ ፡ እግዚአብሔር ቤት፡እንሂድ፡ባሉኝ፡ጊዜ፡ደስ፡አለኝ፡ ፩
ኢየሩሳሌም ፡ ሆይ ፡ እግሮቻችን ፡ በአደባባይሽ ፡ ቆሙ ፤ ፪
ኢየሩሳሌምስ ፡ እርስ ፡ በርሷ ፡ እንደ ፡ ተገጠገጠች ፡ ፫
ከተማ ፡ ተሠርታለች ፡
የእግዚአብሔርን፡ ስም ፡ ያመሰግኑ ፡ ዘንድ ፡
ለእስራኤል ፡ ምስክር ፡ ሊሆኑ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፬
ነገዶች ፡ ወደዚያ ፡ ይወጣሉ ።
ዙፋኖች ፡ እዚያ ፡ ለፍርድ ፡ ተዘጋጅተዋልና ፡ ፭
የዳዊት ፡ ቤት ፡ ዙፋኖች ።
ለኢየሩሳሌም ፡ ሰላምን ፡ ፮
አንተንም ፡ ለሚወዱ ፡ ደስታን ፡ ለመኑ ።
በኀይልህ ፡ ሰላም ፡ ፯
በጌጠኛ ፡ ቤትህም ፡ ደስታ ፡ ይሁን ።
ስለ ፡ ወንድሞቼ ፡ ስለ ፡ ባልንጀሮቼም ፡ ፰
በውስጥሽ ፡ ሰላም ፡ ይሁን ፡ አልሁ ።
ስለ ፡ አምላካችን ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ፱
ላንቺ ፡ መልካምነትሽን ፡ ፈለግሁ ።

መዝሙር ፡ ፻፳፫ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

በሰማይ ፡ የምትኖር ፡ ሆይ ፤ ዓይኖቼን ፡ ወደአንተ ፡ አነሣሁ ፤ ፩
እነሆ ፡ የባሮች ፡ ዓይኖች ፡ ወደ ፡ ጌታቸው ፡ ዓይኖች ፡ እንደሆኑ ።
የባሪያዪቱም ፡ ዓይን ፡ ወደ ፡ እመቤቷ ፡ እጅ ፡ ፪
እንደ ፡ ሆነ ፡ እስኪምረን ፡ ድረስ ፡
እንዲሁ ፡ ዓይናችን ፡ ወደ ፡ አምላካችን ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ።
ማረን ፡ አቤቱ ፡ ማረን ፡ ፫
ንቀትን ፡ እጅግ ፡ ጠግበናልና ።
የባለጠጎችን ፡ ስድብ ፡ የትዕቢተኞችን ፡ ንቀት ፡ ፬
ነፍሳችን ፡ እጅግ ፡ ጠገበች ።

መዝሙር ፡ ፻፳፫ ።

በእንተ ትሩፋን ።

፩ ሶበ ፡ አኮ ፡ እግዚአብሔር ፡ ምስሌነ ።
፪ ይብል፡ እስራኤል፡ሶበ፡ አኮ፡እግዚአብሔር ፡ ምስሌነ
እንተ ፡ጊዜ ፡ ተንሥአ ፡ ሰብእ ፡ ላዕሌነ ።
አሐዝብ ፡ ሕያዋኒነ ፡ እምውኅጡነ ።
፫ በከመ ፡ አንሥኡ ፡ ቍጥዓ ፡ መዓቶሙ ፡ ላዕሌነ ።
፬ አሐዝብ ፡ በማይ ፡ እምአስጠሙነ ።
እምውኂዝ ፡ እምስጠት ፡ ነፍስነ ።
፭ እምሰጠት ፡ ነፍስነ ፡ እማየ ፡ ሀከክ ።
ይትባረክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እምላክነ ።
፮ ዘኢያግብአነ ፡ ውስተ ፡ መሥገርተ ፡ ማዕገቶሙ ።
፯ ነፍስነሰ፡አምስጠት፡ከመ፡ዖፍ፡እመሥገርት፡ነዓዊት ።
መሥገርትሰ ፡ ተቀጥቀጠት ፡ ወንሀነሰ ፡ ድኅነ ።
፰ ረድኤትነሰ ፡ በስመ ፡ እግዚአብሔር ።
ዘገብረ ፡ ሰማየ ፡ ወምድረ ።

መዝሙር ፡ ፻፳፬ ።

በእንተ ትሩፋን ።

፩ እለ ፡ተወከሉ ፡ በእግዚአብሔር፡ ከመ ፡ ደብረ ፡ ጽዮን
ወኢይትሐወክ፡ለዓለም፡ዘየኀድር፡ውስተ፡ኢየሩሳሌም።
፪ አድባር፡የዐውዳ፤ ወእግዚአብሔር ፡ይሜግብ፡ሕዝበ ።
እምይእዜ ፡ ወእስከ ፡ ለዓለም ።
እስመ ፡ ኢየኀድግ ፡ እግዚአብሔር፡ በትረ ፡ ኃጥአን
ዲበ ፡ መክፈልተ ፡ ጻድቃን ።
፫ ከመ ፡ ኢያንሥኡ ፡ እደዊሆሙ ፡ ጻድቃን ፡ በዓመፃ ።
፬ አሠኒ ፡ እግዚኦ ፡ ለኄራን ፡ ወለርቱዓነ ፡ ልብ ።
፭ ወእለሰ ፡ ይትመየጡ ፡ ውስተ ፡ ጌጋ ።
ይወስዶሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ ምስለ ፡ ገበርተ ፡ ዐመፃ
ሰላም ፡ ላዕለ ፡ እስራኤል ።

መዝሙር ፡ ፻፳፭ ።

በእንተ ትሩፋን ።

፩ እመ ፡ ሜጠ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጼዋ ፡ ጽዮን ።
ወኮነ ፡ ፍሡሐነ ።
፪ አሚሃ ፡ መልአ ፡ ፍሥሐ፡ አፉነ ። ወተሐሥየ፡ ልሳንነ ።
አሚሃ ፡ ይቤሉ ፡ አሕዛብ ።
፫ አዕበየ ፡ ገቢረ ፡ ሎሙ ፡ እግዚአብሔር ።
ወኮነ ፡ ፍሡሐነ ።
ሚጥ ፡ እግዚኦ ፡ ጼዋነ ።
፬ ከመ ፡ ውኂዝ ፡ ውስተ ፡ አዜብ ።
፭ እለ ፡ ይዘርዑ ፡ በአንብዕ ፡ ወበሐሤት ፡ የዐርሩ።
፮ ሶበሰ ፡ የሐውሩ ፡ ወፈሩ ፡ እንዘ ፡ ይበክዩ ።
ወጾሩ ፡ ዘርዖሙ ።
ወሶበ ፡ የአትዉ ፡ መጽኡ ፡ እንዘ ፡ ይትፌሥሑ ።
ወጾሩ ፡ ከላስስቲሆሙ ።

መዝሙር ፡ ፻፳፮ ።

በእንተ ትሩፋን ።

፩ እመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ኢሐነጸ ፡ ቤተ ።
ከንቶ ፡ ይጻምዉ ፡ እለ ፡ የሐንጹ ።
እመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ኢዐቀበ ፡ ሀገረ ።
ከንቶ ፡ ይትጌሁ ፡ እለ ፡ ይሔልዉ ።
፪ ወከንቱ ፡ ገይሶትክሙ ።
ተንሥኡ ፡ እምድኅረ ፡ ነበርክሙ ።
እለ ፡ ትሴሰዩ ፡ እክለ ፡ ሕማም ።
ሶበ ፡ ይሁቦሙ ፡ ንዋመ ፡ ለፍቁራኒሁ ።
፫ ናሁ ፡ ጸጋሁ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ውሉድ ።
ዕሴተ ፡ ፍሬሃ ፡ ለከርሥ ።
፬ ከመ ፡ አሕጻ ፡ ውስተ ፡ እደ ፡ ኃያል ።
ከማሁ ፡ ደቂቆሙ ፡ ለንጉፋን ።



መዝሙር ፡ ፻፳፫ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

እግዚአብሔር ፡ ከእኛ ፡ ጋራ ፡ ባይሆን ፡ ፩
እስራኤል፡ እንዲህ ፡ ይበል ።
እግዚአብሔር ፡ ከእኛ ፡ ጋራ ፡ ባይሆን ፡ ፪
ሰዎች ፡ በእኛ ፡ ላይ ፡ በተነሡ ፡ ጊዜ ።
ቍጣቸው ፡ በላያችን ፡ በነደደ ፡ ጊዜ ፡ ፫
በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ሕያዋን ፡ ሳለን ፡ በዋጡን ፡ ነበር ፤
በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ውሀ ፡ ባሰጠመን ፡ ነበር ፤ ፬
በነፍሳችንም ፡ ላይ ፡ ፈሳሽ ፡ በአለፈ ፡ ነበር።
በዚያን፡ጊዜ ፡ የጕርጥ ፡ ውሀ ፡ በነፍሳችን፡ላይ ፡ በአለፈ ፡ ነበር ። ፭
ለጥርሳቸው ፡ ንክሻ ፡ ያላደረገን እግዚአብሔር ፡ ይባረክ ፡ ፮
ነፍሳችን ፡ እንደወፍ ፡ ከአዳኞች ፡ ወጥመድ ፡ አመለጠች ፡ ፯
ወጥመድ ፡ ተሰበረ ፡ እኛም ፡ አመለጥን ።
ረድኤታችን ፡ ሰማይና ፡ ምድርን ፡ በሠራ ፡ ፰
በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ነው ።

መዝሙር ፡ ፻፳፬ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

በእግዚአብሔር ፡ የታመኑ ፡ ፩
እንደማይታወክ ለዘላለም እንደሚኖር እንደ ጽዮን ተራራ ናቸው ።
ተራሮች ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ዙሪያ ፡ እንደሆኑ ፡ ፪
ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ ለዘላለም ፡
እግዚአብሔር ፡ በሕዝቡ ፡ ዙሪያ ፡ ነው ።
ጻድቃን ፡ እጃቸውን ፡ ወደክፋት ፡ እንዳይዘረጉ ፡ ፫
የኃጥአን ፡ በትር ፡ በጻድቃን ፡ ዕጣ ፡ ላይ ፡ አይኖርም ።
አቤቱ ፡ ለቸሮች ፡ ልባቸውም ፡ ለቀና ፡ መልካምን ፡ አድርግ ። ፬
ወደጠማማነት ፡ የሚመለሱትን ፡ ግን ፡ ፭
አመፅን ፡ ከሚሠሩ ፡ ጋር ፡ እግዚአብሔር ፡ ይወስዳቸዋል ።
ሰላም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ይሁን ።

መዝሙር ፡ ፻፳፭ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

እግዚአብሔር ፡ የጽዮንን ፡ ምርኮ ፡ በመለሰ ፡ ጊዜ ፡ ፩
እንደ ፡ ተጽናና ፡ ሰው ፡ ሆንን ።
በዚያን ፡ ጊዜ ፡ አፋችን ፡ ደስታን ፡ ፪
እንደበታችንም ፡ ሐሤትን ፡ መላ ፤
በዚያን ፡ ጊዜ ፡ በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፤
እግዚአብሔር ፡ ታላቅ፡ ነገርን፡ አደረገላቸው ፡ ተባለ ፤ ፫
እግዚአብሔር ፡ ታላቅ፡ነገርን፡ አደረገልን፡ደስም፡አለን ።
አቤቱ ፡ በደቡብ ፡ እንዳሉ ፡ ፈሳሾች ፡ ፬
ምርኳችንን ፡ መልስ ።
በልቅሶ ፡ የሚዘሩ ፡ በደስታ ፡ ያጭዳሉ ፡ ፭
በሄዱ፡ጊዜ፡እያለቀሱ፡ተሰማሩ፡ዘራቸውንም፡ተሸከሙ ፡ ፮
በተመለሱ ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ ደስ ፡ እያላቸው ፡ መጡ ፡
ነዶዋቸውንም ፡ ተሸከሙ ።

መዝሙር ፡ ፻፳፮ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

እግዚአብሔር ቤትን ፡ ካልሠራ ፡ ፩
ሠራተኞች ፡ በከንቱ ፡ ይደክማሉ ፡
እግዚአብሔር ፡ አገርን ፡ ካልጠበቀ ፡
ጠባቂ ፡ በከንቱ ፡ ይተጋል ።
በማለዳ ፡ መገሥገሣችሁም ፡ ከንቱ ፡ ነው ፡ ፪
ለወዳጆቹ ፡ ዕንቅልፍን ፡ በሰጠ ፡ ጊዜ ፡
እናንተ ፡ የመከራን ፡ እንጀራ ፡ የምትበሉ ፡
ከተቀመጣችሁበት ፡ ተነሡ ።
እነሆ ፡ ልጆች ፡ የእግዚአብሔር ፡ ስጦታ ፡ ናቸው ፡ ፫
የሆድም ፡ ፍሬ ፡ የእርሱ ፡ ዋጋ ፡ ነው ።
በኃይለኛ ፡ እጅ ፡ እንዳሉ ፡ ፍላጾች ፡ ፬
የጐልማሳነት ፡ ልጆች ፡ እንዲሁ ፡ ናቸው ።

፭ ብፁዕ ፡ ብእሲ ፡ ዘይፌጽም ፡ ፍትወቶ ፡ እምኔሆሙ ።
ወኢይትኀፈር ፡ ሶበ ፡ ይትናገሮሙ ፡ ለጸላእቱ ፡ በአናቅጽ ።

መዝሙር ፡ ፻፳፯ ።

በእንተ ትሩፋን ።

፩ ብፁዓን ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይፈርህዎ ፡ ለእግዚአብሔር
ወእለ ፡ የሐውሩ ፡ በፍናዊሁ ።
፪ ፍሬ ፡ ፃማከ ፡ ተሴሰይ ። ብፁዕ ፡ አንተ ፡ ወሠናይ ፡ ለከ ።
፫ ብእሲትከ ፡ ከመ ፡ ወይን ፡ ሥሙር ፡ ውስተ ፡ ጽርሐ ፡ ቤትከ ።
ወውሉድከ ፡ ተክለ ፡ ዘይት ፡ ሐዲስ ፡ ዐውደ ፡ ማዕድከ
፬ ናሁ ፡ ከመዝ ፡ ይትባረክ ፡ ብእሲ ፡ ዘይፈርሆ ፡ ለእግዚአብሔር ።
፭ ይባርከ ፡ እግዚአብሔር ፡ እምጽዮን ።
ወትሬኢ ፡ ሠናይታ ፡ ለኢየሩሳሌም ።
በኵሉ ፡ መዋዕለ ፡ ሕይወትከ ።
፮ ወትሬኢ ፡ ውሉደ ፡ ውሉድከ ።
ሰላም ፡ ላዕለ ፡ እስራኤል ።

መዝሙር ፡ ፻፳፰ ።

በእንተ ትሩፋን ።

፩ ዘልፈ ፡ ይጸብኡኒ ፡ እምንዕስየ ።
፪ ይብል ፡ እስራኤል ፡ ዘልፈ ፡ ይጸብኡኒ ፡ እምንእስየ ።
ወባህቱ ፡ ኢክህሉኒ ።
፫ ዲበ ፡ ዘባንየ ፡ ዘበጡ ፡ ኃጥአን ።
ወአስተርኃቅዋ ፡ ለኃጢአቶሙ ።
፬ እግዚአብሔር ፡ ጻድቅ ፡ ሰበረ ፡ አሕዳፊሆሙ ፡ ለኃጥአን ።
ይትኃፈሩ ፡ ወይግብኡ ፡ ድኅሬሆሙ ።
፭ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይጸልእዋ ፡ ለጽዮን ።
፮ ወይኩኑ ፡ ከመ ፡ ሣዕረ ፡ አንሕስት ።
ዘይየብስ ፡ ዘእንበለ ፡ ይምሐውም ።
፯ ወኢይመልዕ ፡ እዴሁ ፡ ለዘየዐጽዶ ።
ወኢሕፅኖ ፡ ለዘያስተጋብእ ፡ ከላስስቲሁ ።
፰ ወኢይበሉ ፡ እለ ፡ የኀልፉ ፡ በረከተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ምስሌነ ።
ባረክናክሙ ፡ በስመ ፡ እግዚአብሔር ።

መዝሙር ፡ ፻፳፱ ።

በእንተ ትሩፋን ።

፩ እምዕምቅ ፡ ጸዋዕኩከ ፡ እግዚኦ ።
፪ እግዚኦ ፡ ስምዐኒ ፡ ቃልየ ።
ወይኩን ፡ እዝንከ ፡ ዘያጸምዕ ፡ ቃለ ፡ ስእለትየ ።
፫ እመሰ ፡ ኀጢአተኑ ፡ ትትዓቀብ ።
እግዚኦ ፡ እግዚኦ ፡ መኑ ፡ ይቀውም ።
፬ እስመ ፡ እምኀቤከ ፡ ውእቱ ፡ ሣህል ።
፭ በእንተ ፡ ስምከ ፡ ተሰፈውኩከ ፡ እግዚኦ ።
ተዐገሠት ፡ ነፍስየ ፡ በሕግከ ።
ተወከለት ፡ ነፍስየ ፡ በእግዚአብሔር ።
፮ እምሰዐተ ፡ ጽባሕ ፡ እስከ ፡ ሌሊት ።
እምሰዓተ ፡ ጽባሕ ፡ ተወከለ ፡ እስራኤል ፡ በእግዚአብሔር
፯ እስመ ፡ እምኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሣህል ።
ወብዙኅ ፡ አድኅኖ ፡ በኀቤሁ ።
፰ ወውእቱ ፡ ያድኅኖ ፡ ለእስራኤል ፡ እምኵሉ ፡ ኀጢአቱ



ከአንርሱ ፡ ዘንድ ፡ ምኞቱን ፡ የሚፈጽም ፡ ብፁዕ ፡ሰው ፡ ነው ፡ ፭
ጠላቶቻቸውን ፡ በአደባባይ ፡ በተናገሩ ፡ ጊዜ ፡ እርሱ ፡ አያፍርም ።

መዝሙር ፡ ፻፳፯ ።

ስለ ትሩፋን ።

እግዚአብሔርን ፡ የሚፈሩት ፡ ሁሉ ፡ ፩
በመንገዱቹም ፡ የሚሄዱ ፡ ምስጉኖች ፡ ናቸው ።
የድካምህን ፡ ፍሬ ፡ ትመገባለህ ፡ ፪
ምስጉን ፡ ነህ ፡ መልካምም ፡ ይሆንልሃል ።
ሚስትህ ፡ በቤትህ ፡ እልፍኝ ፡ ውስጥ ፡ እንደሚያፈራ ፡ ወይን ፡ ናት ። ፫
ልጆችህ ፡ በማዕድህ ፡ ዙሪያ ፡ እንደ ፡ ወይራ ፡ ቡቃያ ፡ ናቸው ።
እነሆ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈራ ፡ ሰው ፡ እንዲህ ፡ ይባረካል ፬
እግዚአብሔር ፡ ከጽዮን ፡ ይባርክህ ፡ ፭
በሕይወትህ ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ።
የኢሩሳሌምን ፡ መልካምነቷን ፡ ታያለህ ።
የልጆችህንም ፡ ልጆች ፡ ታያለህ ፡ ፮
በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ሰላም ፡ ይሁን ።

መዝሙር ፡ ፻፳፰ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

እስራኤል ፡ ከትንሽነቴ ፡ ጀምሮ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ተሰለፉብኝ ፡ ይበል ። ፩
ከትንሽነቴ ፡ ጀምሮ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ተሰለፉብኝ ፡ ፪
ነገር ፡ ግን ፡ አላሸነፉኝም ።
ኀጢአተኞች ፡ በጀርባዬ ፡ ላይ ፡ መቱ ፡ ፫
ኀጢአታቸውንም ፡ አስረዘሚት ።
እግዚአብሔር ፡ ጻድቅ ፡ ነው ፡ ፬
የኀጢአተኞችን ፡ አንገታቸውን ፡ ቆረጠ ።
ጽዮንን ፡ የሚጠሉ ፡ ሁሉ ይፈሩ ፤ ወደኋላቸውም ፡ ይመለሱ ። ፭
በግንብ ፡ ቤት ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ በቀለ ፡ ሣር ፡ ይሁኑ ፡ ፮
ሳይታጨድ ፡ እንደሚደርቅ ።
ለሚያጭደው ፡ እጁን ፡ ፯
ነዶዎቹን ፡ ለሚሰበስብ ፡ እቅፉን ፡ እንደማይሞላ ።
በመንገድም ፡ የሚያልፉ ፡ የእግዚአብሔር ፡ በረከት ፡ በእናንተ ፡ ላይ ፡ ይሁን ። ፰
በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ እንመርቃችኋለን ፡ አይሉም ።

መዝሙር ፡ ፻፳፱ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

አቤቱ ፡ አንተን ፡ ከጥልቅ ፡ ጠራሁህ ፡ ፩
አቤቱ ፡ ድምፄን ፡ ስማ ፡ ፪
ጆሮህ ፡ የልመናዬን ፡ ቃል ፡ የሚያደምጥ ፡ ይሁን ።
አቤቱ ፡ ኃጢአትንስ ፡ ብትጠባበቅ ፡ ፫
አቤቱ ፡ ማን ፡ ይቆማል ?
ስለ ፡ ስምህ ፡ ይቅርታ ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡ ነውና ፡ ፬
አቤቱ ፡ ተስፋ ፡ አደረግሁህ ፡ ፭
ነፍሴ ፡ በሕግህ ፡ ታገሠች ።
ከጧት ፡ እስከ ፡ ሌሊት ፡ ፮
ነፍሴ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ታመነች ።
በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ምሕረት ፡ ፯
በእርሱም ፡ ዘንድ ፡ ብዙ ፡ ማዳን ፡ ነውና ፡
ከጧት ፡ ጀምሮ ፡ እስራኤል ፡ በእግዚአብሔር ፡ ይታመን ።
እርሱም ፡ እስራኤልን ፡ ከኃጢአቱ ፡ ሁሉ ፡ ያድነዋል ። ፰

መዝሙር ፡ ፻፴ ።

በእንተ ትሩፋን

፩ እግዚኦ ፡ ኢይትዔበየኒ ፡ ልብየ ።
ወኢይዛዋዕ ፡ አዕይንትየ ።
ወኢሖርኩ ፡ ምስለ ፡ ዐበይት ።
ወኢምስለ ፡ እለ ፡ ይከብሩ ፡ እምኔየ ።
ዘእንበለ ፡ ዘአትሐትኩ ፡ ርእስየ ።
ወከላሕኩ ፡ በቃልየ ።
ከመ ፡ ዘአኀደግዎ ፡ ጥበ ፡ እሙ ።
፪ ከመ ፡ ትዕስየ ፡ ለነፍስየ ።
ተወከለ ፡ እስራኤል ፡ በእግዚአብሔር ።
፫ እምይእዜ ፡ ወእስከ ፡ ለዓለም ።

መዝሙር ፻፴፩ ።
በእንተ ትሩፋን

፩ ተዘከር ፡ እግዚኦ ፡ ለዳዊት ፡ ወለኵሉ ፡ የዋሀቱ ።
፪ ዘከመ ፡ መሐለ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ወበፅዐ ፡ ለአምላከ ያዕቆብ ።
፫ ከመ ፡ ኢይበውእ ፡ ውስተ ፡ ጽላሎተ ፡ ቤትየ ።
ወከመ ፡ ኢየዐርግ ፡ ውስተ ፡ ዐራተ ፡ ምስካብየ ።
፬ ወከመ ፡ ኢይሁቦን ፡ ንዋመ ፡ ለአዕይንትየ ።
ወኢድቃሰ ፡ ለቀራንብትየ ።
ወኢዕረፍተ ፡ ለመላትሒየ ።
፭ እስከ ፡ እረክብ ፡ መካነ ፡ ለእግዚአብሔር ።
ወማኅደረ ፡ ለአምላከ ፡ ያዕቆብ ።
፮ ናሁ ፡ ሰማዕናሁ ፡ በኤፍራታ ።
ወረከብናሁ ፡ ውስተ ፡ ዖመ ፡ ገዳም ።
፯ ንበውእ ፡ እንከሰ ፡ ውስተ ፡ አብያቲሁ ለእግዚአብሔር
ወንስግድ፡ውስተ፡መካን፡ ኀበ፡ቆመ፡ እግረ፡ እግዚእነ ፡
፰ ተንሥእ ፡ እግዚኦ ፡ ውስተ ፡ ዕረፍትከ ።
አንተ ፡ ወታቦተ ፡ መቅደስከ ።
፱ ካህናቲከ ፡ ይለብሱ ፡ ጽድቀ ።
ወጻድቃኒከ ፡ ትፍሥሕተ ፡ ይትፌሥሑ ።
፲ በእንተ ፡ ዳዊት ፡ ገብርከ ።
ወኢትሚጥ ፡ ገጸከ ፡ እመሲሕከ ።
፲፩ መሐለ እግዚአብሔር ለዳዊት፡በጽድቅ፡ወኢይኔስሕ።
እስመ፡ እምፍሬ ፡ ከርሥከ ፡ አነብር፡ ዲበ ፡መንበርከ።
፲፪ ለእመ ፡ ዐቀቡ ፡ ደቂቅከ ፡ ሕግየ ።
ወሰምዑኒ ፡ ዘንተ ፡ ዘእሜህሮሙ ።
ወደቂቆሙኒ፡እስከ፡ለዓለም፡ይነብሩ፡ ዲበ፡መንበርከ ።
፲፫ እስመ ፡ ኀረያ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለጽዮን ።
ወአብደራ ፡ ከመ ፡ ትኩኖ ፡ ማኅደሮ ።
፲፬ ዛቲ ፡ ይእቲ ፡ ምዕራፍየ ፡ ለዓለም ።
ዝየ ፡ አኀድር ፡ እስመ ፡ ኀረይክዋ ።
፲፭ ለዕቤራቲሃኒ ፡ ባርኮ ፡ እባርኮን ።
ወለነዳያኒሃኒ ፡ አጸግቦሙ ፡ እክለ ።
፲፮ ወለካህናቲሃኒ ፡ አለብሶሙ ፡ ሕይወተ ።
ወጻድቃኒሃኒ ፡ ትፍሥሕተ ፡ ይትፌሥሑ ።
፲፯ ወበህየ ፡ አበቊል ፡ ቀርነ ፡ ለዳዊት ።
ወአስተዴሉ ፡ ማኅቶተ ፡ ለመሲሕየ ።
፲፰ ወአለብሶሙ ፡ ኀፍረተ ፡ ለጸላእቱ ።
ወቦቱ ፡ ይፈሪ ፡ ቅድሳትየ ።

መዝሙር ፡ ፻፴፪ ።

በእንተ ትሩፋን

፩ ናሁ ፡ ሠናይ ፡ ወናሁ ፡ አዳም ።
ሶበ ፡ ይሄልዉ ፡ አኃው ፡ ኅቡረ ።
፪ ከመ፡ ዕፍረት፡ ዘይወኅዝ፡ እምርእሱ፡ እስከ፡ጽሕሙ።
ጽሕሙ ፡ ለአሮን ፡ ዘይወርድ ፡ ዲበ፡ ኀባኔ ፡ መልበሱ።



መዝሙር ፡ ፻፴ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

አቤቱ ፡ ል ቤ ፡ አይታበይብኝ ፡ ፩
ዓይኖቼም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አይበሉብኝ ።
ከትልልቆች ፡ ጋራ ፡
ከእኔም ፡ ይበልጥ ፡ ከሚከበሩ ፡ ጋራ ፡ አልሄድሁም ።
ነፍሴን ፡ አሳረፍኋት ፡ ፪
የእናቱንም ፡ ጡት ፡ እንዳስተዉት ፡ ዝም ፡ አሰኘኋት ፡
ነፍሴ፡የናቱን፡ ጡት፡ እንዳስተዉት፡ በእኔ፡ ውስጥ ፡ ናት ።
ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ፫
እስራኤል ፡ በእግዚአብሔር ፡ ይታመን ።

መዝሙር ፡ ፻፴፩ ።
ስለ ፡ ትሩፋን ።

አቤቱ ፡ ዳዊትን ፡ ገርነቱንም ፡ ሁሉ ፡ አስብ ፡ ፩
ለእግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ማለ ፡ ፪
ለያዕቆብም ፡ አምላክ ፡ እንደ ፡ ተሳለ ፡
በእውነት ፡ ወደ ፡ ቤቴ ፡ ድንኳን ፡ አልገባም ፡ ፫
ወደ ፡ ምንጣፌም ፡ አልጋ ፡ አልወጣም ።
ለዓይኖቼም ፡ መኝታ ፡ ለቅንድቦቼም ፡ እንቅልፍ ፡ ፬
ለጉንጮቼም ፡ ዕረፍትን ፡ አልሰጥም ፡
ለእግዚአብሔር ፡ ስፍራ ፡ ፭
ለያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ ማደሪያ ፡ እስካገኝ ፡ ድረስ ፡ ብሎ ።
እነሆ ፡ በኤፍራታ ፡ ሰማነው ፡ ፮
በዱር ፡ ውስጥም ፡ አገኘነው ።
ወደ ፡ ድንኳኖቹ ፡ እንገባለን ፡ ፯
እግሮቹ ፡ በሚቆሙበት ፡ ስፍራ ፡ እንሰግዳለን ።

አቤቱ ፡ ወደ ፡ ዕረፍትህ ፡ ተነሥ ፡ ፰
አንተና ፡ የመቅደስህ ፡ ታቦት ፡
ካህናቶችህ ፡ ጽድቅን ፡ ይልበሱ ፡ ፱
ቅዱሳንህም ፡ ደስ ፡ ይበላቸው ።
ስለ ፡ ዳዊት ፡ ስለ ፡ ባሪያህ ፡ ፲
የመሲሕህን ፡ ፊት ፡ አትመልስ ።
እግዚአብሔር ለዳዊት በእውነት ማለ አይጸጸትም ፡ ፲፩
እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ከሆድህ ፡ ፍሬ ፡ በዙፋንህ ፡ ላይ ፡ አስቀምጣለሁ ።
ልጆችህ ፡ ኪዳኔን ፡ ፲፪
ይህንም ፡ የማስተምራቸውን ፡ ምስክሬን ፡ ቢጠብቁ ፡
ልጆቻቸው ፡ ደግሞ ፡ በዙፋንህ ፡ ላይ ፡ ለዘላለም ፡ ይቀመጣሉ ።
እግዚአብሔር ፡ ጽዮንን ፡ መርጧታልና ፡ ፲፫
ማደሪያውም ፡ ትሆነው ፡ ዘንድ ፡ ወዷታልና ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡
ይህች ፡ ለዘላለም ፡ ማረፊያዬ ፡ ናት ፡ ፲፬
መርጫታለሁና ፡ በዚህች ፡ እድራለሁ ።
አሮጊዎቿን ፡ እጅግ ፡ እባርካለሁ ፡ ፲፭
ድሆቿንም ፡ እንጀራ ፡ እጠግባለሁ ።
ካህናቶቿንም ፡ ደኅንነትን ፡ አለብሳቸዋለሁ ። ፲፮
ቅዱሳኖቿም ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
በዚያ ፡ ለዳዊት ፡ ቀንድን ፡ አበቅላለሁ ፡ ፲፯
ቀብቼ ፡ ላነገሥሁትም ፡ መብራትን ፡ አዘጋጀሁ ።
ጠላቶቹንም ፡ እፍረትን ፡ አለብሳቸዋለሁ ፡ ፲፰
በእርሱ ፡ ግን ፡ ቅድስናዬ ፡ ያብባል ።

መዝሙር ፡ ፻፴፪ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

ወንድሞች ፡ በኅብረት ፡ቢቀመጡ ፡ ፩
እነሆ ፡ መልካም ፡ ነው ፡ በእርግጥም ፡ ያማረ፡ነው ፤
ከራስ ፡ እስከ ፡ ጽሕም ፡ እንደሚፈስ ፡ ፪
እስከ ፡ አሮን ፡ ጽሕም ፡
በልብሱ ፡ መደረቢያም ፡ እንደሚወርድ ፡ ሽቱ ፡ ነው ።

፫ ወከመ ፡ ጠለ ፡ አርሞንኤም ፡ ዘይወርድ ፡ ዲበ ፡
አድባረ ፡ ጽዮን ።
እስመ ፡ ሀየ ፡ አዘዘ ፡ እግዚአብሔርብረከቶ ።
ወሕይወተ ፡ እምይእዜ ፡ ወእስከ ፡ ለዓለም ።

መዝሙር ፡ ፻፴፫ ።

በእንተ ትሩፋን

፩ ናሁ ፡ ይባርክዎ ፡ ለእግዚአብሔር ።
ኵሎሙ ፡ አግብርተ ፡እግዚአብሔር ።
እለ ፡ ይቀውሙ ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ እግዚአብሔር ።
ውስተ ፡ ዐፀደ ፡ ቤተ ፡ አምላክነ ።
፪ በሌሊት ፡ አንሥኡ ፡ እደዊክሙ ፡ በቤተ ፡ መቅደስ ።
ወባርክዎ ፡ ለእግዚአብሔር ።
ይባርክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እምጽዮን ።
፫ ዘገብረ ፡ ሰማየ ፡ ወምድረ ።

መዝሙር ፡ ፻፴፬ ።

በእንተ ትሩፋን

፩ ሰብሑ ፡ ለስመ ፡ እግዚአብሔር ።
ሰብሕዎ ፡ አግብርቲሁ ፡ ለእግዚአብሔር ።
እለ ፡ ይቀውሙ ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ እግዚአብሔር ።
፪ ውስተ ፡ ዐፀደ ፡ ቤተ ፡ አምላክነ ።
፫ ሰብሕዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እስመ ፡ ኄር ፡ እግዚአ
ብሔር ።
ወዘምሩ ፡ ለስሙ ፡ እስመ ፡ ሠናይ ።
፬ እስመ ፡ ለያዕቆብ ፡ ኀረዮ ፡ እግዚአብሔር ።
ወለእስራኤልኒ ፡ ለሎቱ ፡ ለርስቱ ።
፭ እስመ፡አነ ፡ አእመርኩ፡ ከመ፡ ዐቢይ ፡ እግዚአብሔር።
ወአምላክነኒ ፡ እምኵሉ ፡ አማልክት ።
ኵሎ ፡ ዘፈቀደ ፡ ገብረ ፡ እግዚአብሔር ።
፮ በሰማይኒ ፡ ወበምድርኒ ።
በባሕርኒ ፡ ወበኵሉ ፡ ቀላያት ።
፯ ያዐርግ ፡ ደመናተ ፡ እምአጽናፈ ፡ ምድር ።
ወገብረ ፡ መብረቀ ፡ ለጊዜ ፡ ዝናም ።
ዘያወፅኦሙ ፡ ለነፋሳት ፡ እመዛግብቲሆሙ ።
፰ ዘቀተለ ፡ ኵሎ ፡ በኵሮሙ ፡ ለግብጽ ።
እምሰብእ ፡ ወእስከ ፡ እንስሳ ።
፱ ፈነወ ፡ ተአምረ ፡ ወመንክረ ፡ ማእከሌኪ ፡ ግብጽ ።
ላዕለ ፡ ፈርዖን ፡ ወላዕለ ፡ አግብርቲሁ ።
፲ ዘቀተለ፡አሕዛበ፡ብዙኃነ።ወቀተለ፡ነገሥተ፡ ጽኑዓነ ።
፲፩ ለሴዎን ፡ ንጉሠ ፡ አሞሬዎን ።
ወለዐግ ፡ ንጉሠ ፡ ባሳን ።
ወለኵሎሙ ፡ ነገሥተ ፡ ከነዓን ፡
፲፪ ወወሀበ ፡ ምድሮሙ ፡ ርስተ ።
ርስተ ፡ እስራኤል ፡ ገብሩ ።
፲፫ ስምከ ፡ እግዚኦ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ።
ወዝክርከኒ ፡ ለትውልደ ፡ ትውልድ ።
፲፬ እስመ ፡ ይኴንን ፡ እግዚአብሔር ፡ ሕዝቦ ።
ወይትናበብ ፡ በእንተ ፡ አግብርቲሁ ።
፲፭ አማልክቲሆሙ ፡ ለአሕዛብ ፡ ዘወርቅ ፡ ወዘብሩር ።
ግብረ ፡ እደ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ።
፲፮ አፍ ፡ ቦሙ ፡ ወኢይነቡ ።
ዐይን ፡ ቦሙ ፡ ወኢይሬእዩ ።
፲፯ እዝን ፡ ቦሙ ፡ ወኢይሰምዑ ።
እንፍ ፡ ቦሙ ፡ ወኢያጼንዉ ።
እድ ፡ ቦሙ ፡ ወኢይገሡ ።
እግር ፡ ቦሙ ፡ ወኢየሐውሩ ።
ወኢይነቡ ፡ በጐራዒቶሙ ።
ወአልቦ ፡ መንፈስ ፡ ውስተ ፡ አፉሆሙ ።



በጽዮን ፡ ተራሮች ፡ እንደሚወርድ ፡ እንደ ፡ ፫
አርሞንኤም ፡ ጠል ፡ ነው ፡
በዚያ ፡ እግዚአብሔር ፡ በረከቱን ፤
ሕይወትንም ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ አዞአልና ።

መዝሙር ፡ ፻፴፫ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

እነሆ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ባርኩ ፡ ፩
በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አደባባዮች ፡ የምትቆሙ ፡
ሁላችሁ ፡ እናንተ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ባሮች ።
በሌሊት፡በቤተ፡መቅደስ፡ውስጥ፡ እጆቻችሁን፡አንሡ ፡ ፪
እግዚአብሔርንም ፡ ባርኩ ።
ሰማይንና ፡ ምድርን ፡ የሠራ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፫
ከጽዮን ፡ ይባርክህ ።

መዝሙር ፡ ፻፴፬ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

ሃሌ ፡ ሉያ ፤
የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ አመስግኑ ፡ ፩
እናንተ ፡የእግዚአብሔር ፡ ባሮች ፡ ሆይ ፡ አመስግኑት ።
በአምላካችን ፡ ቤት ፡ ስፍራ ፡ ፪
በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ የምትቆሙ ።
እግዚአብሔርቸር፡ነውና፡ እግዚአብሔርንአመስግኑ ፡ ፫
መልካም ፡ ነውና ፡ ለስሙ ፡ ዘምሩ ።
እግዚአብሔር ፡ያዕቆብን ፡ ለራሱ ፡ ፬
እስራኤልንም ፡ ለገንዘቡ ፡ መርጦታልና ።
እግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፡ እንደሆነ ፡ ፭
ጌታችንም ከአማልክት ሁሉ እንዲበልጥ አውቃለሁና ።
በሰማይና ፡ በምድር ፡ በባሕርና ፡ በጥልቆች ፡ ሁሉ ፡ ፮
እግዚአብሔር ፡ የወደደውን ፡ ሁሉ ፡ አደረገ ።
ከምድር ፡ ዳር ፡ ደመናትን ፡ ያወጣል ፡ ፯
በዝናብ ፡ ጊዜ ፡ መብረቅን ፡ አደረገ ፤
ነፋሳትንም ፡ ከወንዞች ፡ ያወጣል ።
የግብጽን ፡ በኵር ፡ ልጆች ፡ ፰
ከሰው ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ እንስሳት ፡ ድረስ ፡ መታ ።
ግብጽ፡ሆይ፡በመካከልሽ፡በፈርዖንና፡በባሮቹ፡ሁሉ፡ላይ ፡ ፱
ተአምራትንና ፡ ድንቅን፡ሰደደ ። ብዙ፡አሕዛብን፡መታ፡
ብርቱዎችንም ፡ ነገሥታት ፡ ገደለ ። ፲
የአሞራውያንን ፡ ንጉሥ ፡ ሴዎንን ፡ የባሳንንም ፡ ንጉሥ ፡ ዐግን ፡ ፲፩
የከነዓንን ፡ መንግሥታት ፡ ሁሉ ፡ ገደለ ።
ምድራቸውንም ፡ ርስት ፡ አድርጎ ፡ ፲፪
ለእስራኤል ፡ ለሕዝቡ ፡ ርስት ፡ ሰጠ ።
አቤቱ ፡ ስምህ ፡ ለዘላለም ፡ ነው ፡ ፲፫
መታሰቢያህም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ነው ።
እግዚአብሔር ፡ ለሕዝቡ ፡ ይፈርዳልና ፡ ፲፬
ባሮቹንም ፡ ይረዳል ።
የአሕዛብ ፡ ጣዖታት ፡ የብርና ፡ የወርቅ ፡ ፲፭
የሰው ፡ እጅ ፡ ሥራ ፡ ናቸው ።
አፍ ፡ አላቸው ፡ አይናገሩም ፡ ፲፮
ዓይን ፡ አላቸው ፡ አያዩም ።
ጆሮ ፡ አላቸው ፡ አይሰሙም ፡ ፲፯
እስትንፋስም ፡ በአፋቸው ፡ የለም ።

፲፰ ከማሆሙ ፡ ለይኩኑ ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ ገብርዎሙ ።
ወኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይትአመኑ ፡ በሙ ።
፲፱ ቤተ ፡ እስራኤል ፡ ባርክዎ ፡ ለእግዚአብሔር ።
ቤተ ፡ አሮን ፡ ባርክዎ ፡ እግዚአብሔር ።
፳ ቤተ ፡ ሌዊ ፡ ባርክዎ ፡ ለእግዚአብሔር ።
እለ ፡ ትፈርህዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ባርክዎ ፡ ለእግዚአብሔር ።
ቡሩክ ፡ እግዚአብሔር፡ በጽዮን ።
፳፩ ዘየኀድር ፡ ውስተ ፡ ኢየሩሳሌም ።

መዝሙር ፡ ፻፴፭ ።

በእንተ ትሩፋን

፩ ግነዩ ፡ ለእግዚአብሔር፡ እስመ ፡ ኄር ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፪ ግነዩ ፡ ለአምላከ ፡ አማልክት ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፫ ግነዩ ፡ ለእግዚአ ፡ አጋዕዝት ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፬ ዘገብረ ፡ ዐቢየ ፡ ወመንክረ ፡ ባሕቲቱ ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፭ ዘገብረ ፡ ሰማያተ ፡ በጥበቡ ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፮ ዘአጽንዓ ፡ ለምድር ፡ ዲበ ፡ ማይ ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፯ ዘገብረ ፡ ብርሃናተ ፡ ዐበይተ ፡ ባሕቲቱ ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፰ ለፀሓይ ፡ ዘአኰነና ፡ መዓልተ ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፱ ለወርኅ ፡ ወለከዋክብት ፡ ዘአኰነኖሙ ፡ ሌሊተ ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፲ ዘቀቀተሎሙ ፡ ለግብጽ ፡ ምስለ ፡ በኵሮሙ ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፲፩ ወአውፅኦሙ ፡ ለእስራኤል ፡ እማእከሎሙ ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፲፪ በእድ ፡ ጽንዕት ፡ ወበመዝራዕት ፡ ልዕልት ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፲፫ ዘነፈቃ ፡ ለባሕረ ፡ ኤርትራ ፡ ወከፈላ ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፲፬ ወአውፅኦሙ ፡ ለእስራኤል ፡ እንተ ፡ ማእከላ ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፲፭ ዘነዕዎ ፡ ለፈርዖን ፡ ወለኀይሉ ፡ ውስተ ፡ ባሕረ ፡ ኤርትራ ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፲፮ ወአውፅኦሙ ፡ ለሕዝቡ ፡ ውስተ ፡ ገዳም ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፲፯ ዘአውፅአ ፡ ማየ ፡ እምኰኵሕ ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፲፰ ዘቀተለ ፡ ነገሥተ ፡ ዐበይተ ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፲፱ ወቀተለ ፡ ነገሥተ ፡ ጽኑዓነ ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፳ ለሴዎን ፡ ንጉሠ ፡ አሞሬዎን ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፳፩ ወለዐግ ፡ ንጉሠ ፡ ባሳን ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፳፪ ወወሀበ ፡ ምድሮሙ ፡ ርስተ ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፳፫ ርስተ ፡ እስራኤል ፡ ገብሩ ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።



የሚሠሯቸው ፡ ሁሉ ፡ ፲፰
የሚታመኑባቸውም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ እነርሱ ፡ ይሁኑ ።
የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ባርኩት ። ፲፱
የአሮን ፡ ቤት፡ሆይ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ባርኩት ።
የሌዊ ፡ ቤት ፡ ሆይ ፡ እግዚአብሔርን፡ባርኩት ፡ ፳
እግዚአብሔርን የምትፈሩት፡ እግዚአብሔርን ባርኩት።
በኢየሩሳሌም ፡ የሚያድር ፡ እግዚአብሔር ፡ ፳፩
ከጽዮን ፡ የተባረከ ፡ ነው ።
ሃሌ ፡ ሉያ ።

መዝሙር ፡ ፻፴፭ ።

ስለ ትሩፋን ።

እግዚአብሔርን አመስግኑ ፡ ቸር ፡ ነውና ፡ ፩
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
የአማልክትን ፡ አምላክ ፡ አመስግኑ ፡ ፪
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
የጌቶችን ፡ ጌታ ፡ አመስግኑ ፡ ፫
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
እርሱ ፡ ብቻውን ፡ ታላቅ ፡ ተአምራትን ፡ ያደረገ ፡ ፬
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
ሰማያትን ፡ በብልሃት ፡ የሠራ ፡ ፭
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
ምድርን ፡ በውሃ ፡ ላይ ፡ ያጸና ፡ ፮
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
ብቻውን ፡ ታላላቅ ፡ ብርሃናትን ፡ የሠራ ፡ ፯
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
ለፀሐይ ፡ ቀንን ፡ ያስገዛው ፡ ፰
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
ለጨረቃና ፡ ለከዋክብትም ፡ ሌሊትን ፡ ያስገዛቸው ፡ ፱
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
ከበኵራቸው ፡ ጋራ ፡ ግብጽን ፡ የመታ ፡ ፲
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
እስራኤልንም ፡ ከመካከላቸው ፡ ያወጣ ፡ ፲፩
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
በጸናች ፡ እጅ ፡ በተዘረጋችም ፡ ክንድ ፡ ፲፪
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
የኤርትራን ፡ ባሕር ፡ በየክፍሉ ፡ የከፈለ ፡ ፲፫
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
እስራኤልን ፡ በመካከሉ ፡ ያሳለፈ ፡ ፲፬
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
ፈርዖንንና ፡ ሠራዊቱን ፡ በኤርትራ ፡ ባሕር ፡ የጣለ ፡ ፲፭
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
ሕዝቡን ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ የመራ ፡ ፲፮
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
ውሀን ፡ ከአለት ፡ ድንጋይ ፡ ያፈለቀ ፡ ፲፯
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
ታላላቅ ፡ ነገሥታትን ፡ የመታ ፡ ፲፰
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
ብርቱዎችንም ፡ ነገሥታት ፡ የገደለ ፡ ፲፱
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
የአሞራውያንን ፡ ንጉሥ ፡ ሴዎንን ፡ ፳
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
የባሳንን ፡ ንጉሥ ፡ ዐግን ፡ ፳፩
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
ምድራቸውን ፡ ርስት ፡ አድርጎ ፡ የሰጠ ፡ ፳፪
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
ለባሪያው ፡ ለእስራኤል ፡ ርስት ፡ ፳፫
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።

፳፫ እስመ ፡ ተዘከረነ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሕማምነ ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፳፬ ወአድኀነነ ፡ እምእደ ፡ ፀርነ ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፳፭ ዘይሁብ ፡ ሲሳየ ፡ ለኵሉ ፡ ዘሥጋ ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።
፳፮ ግነዩ ፡ ለአምላከ ፡ ሰማይ ።
እስመ ፡ ለዓለም ፡ ምሕረቱ ።

መዝሙር ፡ ፻፴፯ ።
በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ ውስተ ፡ አፍላገ ፡ ባቢሎን ፡ ህየ ፡ ነበርነ ፡ ወበከይነ ።
ሶበ ፡ ተዘከርናሃ ፡ ለጽዮን ።
፪ ውስተ ፡ ኵሓቲሃ ፡ ሰቀልነ ፡ እንዚራቲነ ።
፫ እስመ ፡ በህየ፡ተስእሉነ፡እለ፡ፄወዉነ፡ነገረ፡ማኅሌት ፡
ወእለሂ ይወስዱነ፡ይቤሉ ኀልዩ ለነ እመኃልዪሃ ለጽዮን
፬ እፎ ፡ ነኀሊ፡ማኅሌተ፡ እግዚአብሔር ፡ በምድር፡ነኪር
፭ እመሰ ፡ ረሳዕኩኪ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ለትርስዐኒ ፡ የማንየ
፮ ወይጥጋዕ፡ ልሳንየ፡ በጕርዔየ፡ ለእመ፡ ኢተዘከርኩኪ።
ወለእመ ፡ ይበፃእኩ ፡ ለኢየሩሳሌም ፡ በቀዳሚ ፡ ትፍሥሕትየ ።
፯ ተዘከሮሙ ፡ እግዚኦ ፡ ለደቂቀ ፡ ኤዶም ፡ በዕለተ ፡ ኢየሩሳሌም ።
እለ፡ይብሉ፡ተከዕዉ፡ወተሰዉጡ፡ እስከ፡ መሠረታቲሃ ።
፰ ወለተ ፡ ባቢሎን ፡ ኅሥርት ።
ብፁዕ ፡ ዘይትቤቀለኪ ፡ በቀለ ፡ ተበቀልክነ ።
፱ ወብፁዕ ፡ ዘይኀዝሞሙ ፡ ለደቂቅኪ ፡ ወይነፅሮሙ ፡ ውስተ ፡ ኰኵሕ ።

መዝሙር ፡ ፻፴፰ ።
በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ እገኒ ፡ ለከ ፡ እግዚኦ ፡ በኵሉ ፡ ልብየ ።
እስመ ፡ ሰማዕከኒ ፡ ኵሎ ፡ ቃለ ፡ አፉየ ።
በቅድመ ፡ መላእክቲከ ፡ እዜምር ፡ ለከ ።
፪ ወእሰግድ ፡ ውስተ፡ጽርሐ፡መቅደስከ።ወእገኒ፡ለስምከ
በምሕረትከ ፡ ወበጽድቅከ ።
እስመ ፡ አዕበይከ ፡ ዲበ ፡ ኵሉ ፡ ስመከ ፡ ቅዱሰ ።
፫ አመ ፡ ዕለተ ፡ እጼውዐከ ፡ ፍጡነ ፡ ስምዐኒ ።
ብዙኀ ፡ አጽናዕከ ፡ ለነፍስየ ፡ በኀይልከ ።
፬ ይገንዩ ፡ ለከ ፡ እግዚኦ ፡ ኵሎሙ ፡ ነገሥተ ፡ ምድር ።
እስመ ፡ ሰምዑ ፡ ኵሎ ፡ ቃለ ፡ አፉከ ።
፭ ወየኀልዩ ፡ በስብሐተ ፡ እግዚአብሔር ።
እስመ ፡ ዐቢይ ፡ ግብረ ፡ እግዚአብሔር ።
፮ እስመ፡ልዑል ፡ እግዚአብሔር፡ ወይሬኢ፡ዘበታሕቱ።
ወለነዋኀኒ ፡ እምርኁቅ ፡ የአምሮ ።
፯ እመኒ ፡ ሖርኩ፡ ማእከለ፡ ምንዳቤ፡አንተ፡ታሐይወኒ ።
ዲበ ፡ መዓተ ፡ እሕዛብ ፡ ሰፋሕከ ፡ እደውየ ።
ወአድኀነኒ ፡ የማንከ ።
፰ ወእግዚአብሔር ፡ ይትቤቀል ፡ ሊተ ።
እግዚኦ ፡ ሣህልከ ፡ ለዓለም ።
እግዚኦ ፡ ተግባረ ፡ እደዊከ ፡ ኢትህየይ ።

መዝሙር ፡ ፻፴፱ ።
በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ እግዚኦ ፡ አመከርከኒ ፡ ወአእመርከኒ ።
፪ አንተ ፡ ተአምር ፡ ንብረትየ ፡ ወተንሥኦትየ ።
ወአንተ ፡ ተአምር ፡ ኵሎ ፡ ኅሊና ፡ ልብየ ፡ እምርኁቅ



እኛን ፡ በመዋረዳችን ፡ አስቦናልና ፡ ፳፫
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
ከጠላቶቻችንም ፡ እጅ ፡ አድኖናልና ፡ ፳፬
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
ለሥጋ ፡ ሁሉ ፡ ምግብን ፡ የሚሰጥ ፡ ፳፭
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።
የሰማይን ፡ አምላክ ፡ አመስግኑ ። ፳፮
ምሕረቱ ፡ ለዘላለም ፡ ነውና ።

መዝሙር ፡ ፻፴፯ ።
ስለትሩፋን ።

በባቢሎን ፡ ወንዞች ፡ አጠገብ ፡ እዚያ ፡ ተቀምጠን ፡ ፩
ጽዮንን ፡ በአሰብናት ፡ ጊዜ ፡ አለቀስን ።
በአኻያ ፡ ዛፎቿ ፡ ላይ ፡ መሰንቆቻችንን ፡ ሰቀልን ። ፪
የማረኩን ፡ በዚያ ፡ የዝማሬን ፡ ነገር ፡ ፈለጉብን ፡ ፫
የወሰዱንም ፡ የጽዮንን ፡ ዝማሬ ፡ ዘምሩልን ፡ አሉን ።
የእግዚአብሔርን ፡ ዝማሬ ፡ በልዩ ፡ ምድር ፡ እንዴት ፡ እንዘምራለን ። ፬
ኢየሩሳሌም ፡ ሆይ ፡ ብረሳሽ ፡ ቀኜ ፡ ትርሳኝ ። ፭
ባላስብሽ ፡ ምላሴ ፡ በጕረሮዬ ፡ ይጣበቅ ፡ ፮
በፍጹም ፡ ደስታዬ ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ ባልወድ ።
አቤቱ፡ በኢየሩሳሌም፡ ቀን፡ የኤዶምን፡ ልጆች፡ አስብ ፡ ፯
እስከ ፡ መሠረቷ ፡ ድረስ ፡ አፍርሱ ፡ ያሏትን ።
አንቺ ፡ ጕስቋላ ፡ የባቢሎን ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፡ ፰
ስለተበቀልሽን ፡ የሚበቀልሽ ፡ የተመሰገነ ፡ ነው ።
ሕፃናቶችሽን ፡ ይዞ ፡ በዐለት ፡ ላይ ፡ የሚፈጠፍጣቸው ፡ ፱
የተመሰገነ ፡ ነው ።

መዝሙር ፡ ፻፴፰ ።
ስለትሩፋን ።

አቤቱ ፡ በፍጹም ፡ ልቤ ፡ አመሰግንሃለሁ ፡ ፩
የአፌን ፡ ነገር ፡ ሰምተኸኛልና ፡
በመላእክት ፡ ፊት ፡ እዘምርልሃለሁ ።
ወደ ፡ ቅድስናህ ፡ መቅደስ ፡ እሰግዳለሁ ፡ ፪
በስምህ፡ሁሉ፡ላይ፡ቅዱስነትህን፡ከፍ፡ከፍ፡አድርገሃልና ።
ስለ፡ምሕረትህና፡ስለ፡እውነትህ፡ስምህን፡አመሰግናለሁ ።
በጠራሁህ ፡ ቀን ፡ በፍጥነት ፡ አድምጠኝ ፡ ፫
ነፍሴን ፡ በብዙ ፡ ኃይል ፡ አጸናሃት ።
አቤቱ ፡ የምድር ፡ ነገሥታት ፡ ሁሉ ፡ ያመሰግኑሃል ። ፬
የአፍህን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ሰምተዋልና ።
በእግዚአብሔር ፡ መንገድ ፡ ይዘምራሉ ፡ ፭
የእግዚአብሔርም ፡ ክብር ፡ታላቅ ፡ ነውና ።
እግዚአብሔር ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ነው ፡ ፮
ወደ ፡ ችግረኞችም ፡ ይመለከታል ።
ትዕቢተኞችንም ፡ ከሩቅ ፡ ያውቃል ።
በመከራ ፡ መካከል ፡ እንኳ ፡ ብሄድ ፡ አንተ ፡ ሕያው ፡ ታደርገኛለህ ። ፯
በጠላቶቼ ፡ ቍጣ ፡ ላይ ፡ እጆቼን ፡ ትዘረጋለህ ፡
ቀኝህም ፡ ታድነኛለች ።
እግዚአብሔር ፡ ይበቀልልኛል ፡ ፰
አቤቱ ፡ ምሕረትህ ፡ ለዘላለም ፡ ነው ፡
አቤቱ ፡ የእጆህን ፡ ሥራ ፡ቸል ፡ አትበል ።

መዝሙር ፡ ፻፴፱ ።
ስለትሩፋን ።

አቤቱ ፡ መረመርኸኝ ፡ አወቅኸኝም ፡ ፩
አንተ ፡ መቀመጤንና ፡ መነሣቴን ፡ አወቅህ ፡ ፪
አሳቤን ፡ ሁሉ ፡ ከሩቅ ፡ አስተዋልህ ።

፫ ፍጥረትየ ፡ ወእሥርየ ፡ አንተ ፡ ቀጸዕከ ።
ወኵሎ ፡ ፍናውየ ፡ አንተ ፡ አቅደምከ ፡ አእምሮ ።
፬ ከመ ፡ አልቦ ፡ ቃለ ፡ ዐመፃ ፡ ውስተ ፡ ልሳንየ ።
፭ ናሁ፡አንተ፡እግዚኦ፡አእመርከ፡ኵሎ፡ዘቀዳሚ ወዘደኃሪ
አንተ ፡ ፈጠርከኒ ፡ ወወደይከ ፡ እዴከ ፡ ላዕሌየ ።
፮ ተነክረ ፡ አእምሮትከ ፡ በላዕሌየ ።
ጸንዐተኒ ፡ ወኢይክል ፡ ምስሌሃ ።
፯ አይቴኑ ፡ አሐውር ፡ እመንፈስከ ።
ወአይቴ ፡ እጐይይ ፡ እምቅድመ ፡ ገጽከ ።
፰ እመኒ ፡ ዐረጉ ፡ ውስተ ፡ ሰማይ ፡ ሀየኒ ፡ አንተ ።
ወእመኒ ፡ ወረድኩ ፡ ውስተ ፡ ቀላይ ፡ ሀየኒ ፡ ሀሎከ ።
፱ ወእመኒ ፡ ነሣእኩ ፡ ክንፈ ፡ ከመ ፡ ንስር ።
ወሠረርኩ ፡ እስከ ፡ ማኅለቅተ ፡ ባሕር ።
፲ ሀየኒ ፡ እዴከ ፡ ትመርሐኒ ፡ ወታነብረኒ ፡ የማንከ ።
፲፩ ወዕቤ ፡ ጽልመትኑ ፡ እንጋ ፡ ኬደኒ ።
ወሌሊትኒ ፡ ብሩህ ፡ ውስተ ፡ ትፍሥሕትየ ።
፲፪ እስመ ፡ ጽልመትኒ ፡ ኢይጸልም ፡ በኀቤከ ።
ወሌሊትኒ ፡ ብሩህ ፡ ከመ ፡ መዓልት ።
በአምጣነ ፡ ጽልመታ ፡ ከማሁ ፡ ብርሃና ።
፲፫ እስመ ፡ አንተ ፡ ፈጠርከ ፡ ኵልያትየ ፡ እግዚኦ ።
ወተወከፍከኒ ፡ ከመ ፡ አእምር ።
፲፬ እገኒ ፡ ለከ ፡ እግዚኦ ፡ እስመ ፡ ግሩመ ፡ ተሰባሕከ ።
መንክር ፡ ግብርከ ፡ ወነፍስየ ፡ ትጤይቆ ፡ ጥቀ ።
፲፭ ወኢይትኀባእ፡እምኔከ፡አዕዕምትየ፡ዘገበርከ፡በኅቡእ ።
ወአካልየ ፡ በመትሕተ ፡ ምድር ።
፲፮ ወዘሂ ፡ ገበርኩ ፡ ርእየ ፡ አዕይንቲከ ።
ወኵሉ ፡ ይጸሐፍ ፡ ውስተ ፡ መጽሐፍከ ።
መዓልተ ፡ ይትፈጠሩ ፡ ወኢይሄሉ ፡ እንከ ፡ አሐዱ ፡
እምኔሆሙ ።

፲፯ ወበኀቤየሰ ፡ ፈድፋደ ፡ ክቡራን ፡ አዕርክቲከ ፡ እግዚኦ
ወፈድፋደ ፡ ጸንዑ ፡ እምቀደምቶሙ ።
፲፰ እኄልቆሙ ፡ እምኆፃ ፡ ይበዝኁ ።
ተንሣእኩሂ ፤ ወዓዲ ፡ ሀሎኩ ፡ ምስሌከ ።
፲፱ እመሰ ፡ ቀተልኮሙ ፡ ለኃጥኣን ፡ እግዚኦ ።
እድወ ፡ ደም ፡ ተገሐሡ ፡ እምኔየ ።
፳ እስመ ፡ ይዜኀሩ ፡ በኀሊናሆሙ ።
ወይነሥእዎን ፡ ለአህጉሪከ ፡ በከንቱ ።
፳፩ አኮኑ ፡ ጸላእተከ ፡ ጸላእኩ ፡ እግዚኦ ።
ወተመንሰውኩ ፡ በእንተ ፡ ፀርከ ።
፳፪ ፍጹመ ፡ ጽልአ ፡ ጸላእክዎሙ ፤ ወኮኑኒ ፡ ፀርየ ።
፳፫ ፍትነኒ ፡ እግዚኦ ፡ ወአመክር ፡ ልብየ ።
አመክረኒ ፡ ወርኢ ፡ ፍናውየ ።
፳፬ ወርኢ ፡ እመ ፡ ተረክበ ፡ ዐመፃ ፡ በላዕሌየ ።
ወምርሐኒ ፡ ፍኖተ ፡ ዘለዓለም ።

መዝሙር ፡ ፻፴፱ ።

በእንተ ርእሱ ።

፩ አድኅነኒ ፡ እግዚኦ ፡ እምብእሲ ፡ እኩይ ።
ወእምሰብእ ፡ ዐማፂ ፡ ባልሐኒ ።
፪ እለ ፡ ዐመፃ ፡ መከሩ ፡ በልቦሙ ።
ኵሎ ፡ አሚረ ፡ ይረውዱኒ ፡ ይቅትሉኒ ።
፫ ወአብልሑ ፡ ልሳኖሙ ፡ ከመ ፡ አርዌ ፡ ምድር ።
ሕምዘ ፡ አርዌ ፡ ምድር ፡ ታሕተ ፡ ከናፍሪሆሙ ።
፬ ዕቀበኒ ፡ እግዚኦ ፡ እምእደ ፡ ኃጥኣን ።
ወእምብእሲ ፡ ዐማፂ ፡ አድኅነኒ ።
እለ ፡ መከሩ ፡ ያዕቅጹ ፡ መከየድየ ።
፭ ወኀብኡ ፡ ሊተ ፡ መሥገርተ ፡ ዕቡያን ።
ወሠተሩ ፡ አሕባለ ፡ መሣግር ፡ ለእገርየ ።



ፍለጋዬንና ፡ ዕረፍቴን ፡ አንተ ፡ መረመርህ ፡ ፫
ክፉም ፡ ነገር ፡ በአንደበቴ ፡ እንደሌለ ፡ ፬
መንገዶችን ፡ ሁሉ ፡ ቀድመህ ፡ አወቅህ ።
አቤቱ፡አንተ፡እነሆ፡የቀድሞውንና፡የኋላውን፡አወቅህ ፡ ፭
አንተ ፡ ፈጠርኸኝ ፡ እጅህንም ፡ በላዬ ፡ አደረግህ ።
እውቀትህ ፡ ከእኔ ፡ ይልቅ ፡ ተደነቀ ፡ ፮
በረታች ፡ ወደ ፡ እርሷም ፡ ለመድረስ ፡ አልችልም ።
ከመንፈስህ ፡ ወዴት ፡ እሄዳለሁ ? ፯
ከፊትህስ ፡ ወዴት ፡ እሸሻለሁ ። ?
ወደ ፡ ሰማይ ፡ ብወጣ ፡ አንተ ፡ በዚያ ፡ ነህ ፡ ፰
ወደሲኦልም ፡ ብወርድ ፡ ከዚያ ፡ አለህ ።
እንደ ፡ ንስር ፡ የንጋትን ፡ ክንፍ ፡ ብወስድ ፡ ፱
በባሕር ፡ ማዶም ፡ ብቀመጥ ።
በዚያ ፡ እጅህ ፡ ትመራኛለች ፡ ፲
ቀኝህም ፡ ትይዘኛለች ።
በውኑ ፡ ጨለማ ፡ ትሸፍነኛለች ፡ አልሁ ፡ ፲፩
ሌሊትም ፡ በዙሪያዬ ፡ ብርሃን ፡ ትሆናለች ።
ጨለማ ፡ በአንተ ፡ ዘንድ ፡ አይጨልምምና ፡ ፲፪
ሌሊትም ፡ እንደ ፡ ቀን ፡ ታበራለች ፡
እንደ፡ጨለማም ፡ እንዲሁ ፡ ብርሃኗ ፡ ነው ።
አቤቱ ፡ አንተ ፡ ኵላሊቴን ፡ ፈጥረሃልና ፡ ፲፫
በእናቴም ፡ ሆድ ፡ ሰውረኸኛልና ።
ግሩምና ፡ ድንቅ ፡ ሆኜ ፡ ተፈጥሬአለሁና ፡ አመሰግንሃለሁ ፤ ፲፬
ሥራህ ፡ ድንቅ፡ ነው፡ ነፍሴም፡ እጅግ ፡ ታውቀዋለች ።
እኔ ፡ በስዉር ፡ በተሠራሁ፡ ጊዜ ፡ ፲፭
አካሌም ፡ ከምድር ፡ በታች ፡ በተሠራ ፡ ጊዜ ፡
አጥንቶቼ ፡ ከአንተ ፡ አልተሰወሩም ።
እኔ ፡ ሳልፈጠር ፡ ዓይኖችህ ፡ አዩኝ ፡ ፲፮
የተፈጠሩ ፡ ቀኖቼ ፡ ሁሉ ፤
አንድ ፡ ስንኳ ፡ ሳይኖር ፡ በመጽሐፍ ፡ ተጻፉ ።
አቤቱ ፡ አሳቦችህ ፡ በእኔ ፡ ዘንድ ፡ እንደምን ፡ እጅግ ፲፯
የተከበሩ ፡ ናቸው ፡
ቍጥራቸውም ፡ እንደምን ፡ በዛ ።
ብቈጥራቸውም ፡ ከአሸዋ ፡ ይልቅ ፡ ይበዛሉ ፡ ፲፰
ተነሣሁም ፡ እኔም ፡ ገና ፡ ከአንተ ፡ ጋራ ፡ ነኝ ።
አቤቱ ፡ አንተ ፡ ኃጢአተኞችን ፡ የምትገድል ፡ ከሆንህ ፡ ፲፱
የደም ፡ ሰዎች ፡ ከእኔ ፡ ፈቀቅ ፡ ይበሉ ።
በክፋት ፡ ይናገሩብሃል ፡ ፳
ጠላቶችህ ፡ በከንቱ ፡ ያምፁብሃል ።
አቤቱ ፡ የሚጠሉህን ፡ እኔ፡የጠላሁ ፡ አይደለሁምን ? ፳፩
ስለጠላቶችህም ፡ አልተሰቀቅሁምን ?
ፍጹም ፡ ጥል ፡ ጠላኋቸው ፡ ጠላቶችም ፡ ሆኑኝ ፡ ፳፪
አቤቱ ፡ መርምረኝ ፡ ልቤንም ፡ እወቅ ፡ ፳፫
ፍተነኝ ፡ መንገዴንም ፡ እወቅ ።
በደልም ፡ በእኔ ፡ ውስጥ ፡ ብታገኝ ፡ እይ ፡ ፳፬
የዘላለምንም ፡ መንገድ ፡ ምራኝ ።

መዝሙር ፡ ፻፴፱ ።

ስለራሱ ።

አቤቱ ፡ ከክፉ ፡ ሰው ፡ አድነኝ ። ፩
በልባቸውም ፡ ክፉ ፡ ከአሰቡ ፡ ፪
ከዓመፀኞች ፡ ሰዎች ፡ ጠብቀኝ ፤
ቀኑን ፡ ሁሉ ፡ ለሰልፍ ፡ ይከማቻሉ ።
ምላሳቸውን ፡ እንደ ፡ እባብ ፡ ምላስ ፡ አውለበለቡ ፡ ፫
ከከንፈራቸው ፡ በታች ፡ የእፉኝት ፡ መርዝ ፡ ነው ።
አቤቱ ፡ ከኃጢአተኛ ፡ እጅ ፡ ጠብቀኝ ፡ ፬
እርምጃዬንም ፡ ሊያሰናክሉ ፡ ከመከሩ ፡
ከዓመፀኞች ፡ አድነኝ ።
ትዕቢተኞች ፡ ወጥመድን ፡ ሰወሩብኝ ፡ ፭
ለእግሮቼም ፡ የወጥመድ ፡ ገመድን ፡ ዘረጉ ።

ወአንበሩ ፡ ዕቅፍተ ፡ ውስተ ፡ ፍኖትየ ።
፮ ወእቤሎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አምላኪየ ፡ አንተ ።
ወአጽምዐኒ ፡ ቃለ ፡ ስእለትየ ።
፯ እግዚኦ ፡ እግዚኦ ፡ ኃይለ ፡ መድኃኒትየ ።
ሰወርኮኒ ፡ በዕለተ ፡ ቀትል ፡ መልዕልተ ፡ ርእስየ ።
፰ ኢትመጥወኒ ፡ እግዚኦ ፡ እምፍትወትየ ፡ ለኃጥአን ።
ተማከሩ ፡ ላዕሌየ ፤ ወኢትኅድገኒ ፡ ከመ ፡ ኢይዘኀሩ ።
፱ ርዕሰ ፡ ማዕገቶሙ ። ወፃማ፡ ከናፍሪሆሙ ፡ይድፍኖሙ
፲ ወይደቅ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ አፍሓመ ፡ እሳት ።
ወትንዕኖሙ ፡ ውስተ ፡ ምድር ።
በምንዳቤ ፡ ከመ ፡ ኢይክሀሉ ፡ ቀዊመ ።
፲፩ ብእሲ ፡ ነባቢ ፡ ኢያረትዕ ፡ በዲበ ፡ ምድር ።
ወለብእሲ ፡ ዐማፂ ፡ ትንዕዎ ፡ እኪት ፡ ለአማስኖ ።
፲፪ አእመርኩ ፡ ከመ ፡ ይገብር ፡ እግዚአብሔር ፡
ኰንኖ ፡ ለነዳያን ፡ ወፍትሐ ፡ ለምስኪናን ።
፲፫ ወባሕቱ ፡ ጻድቃን ፡ ይገንዩ ፡ ለስምከ ።
ወይነብሩ ፡ ራትዓን ፡ ቅድመ ፡ ገጽከ ።

መዝሙር ፡ ፻፵ ።

በእንተ ትሩፋን ።

፩ እግዚኦ ፡ ጸራሕኩ ፡ ኀቤከ ፡ ስምዐኒ ።
ወአጽምዖ ፡ ቃለ ፡ ስእለትየ ፡ ዘጸራሕኩ ፡ ኀቤከ ።
፪ ተወከፈኒ ፡ ጸሎትየ ፡ ከመ ፡ ዕጣን ፡ በቅድሜከ ።
አንሥኦ ፡ እደውየ ፡ መሥዋዕተ ፡ ሠርክ ።
፫ ሢም ፡ እግዚኦ ፡ ዐቃቤ ፡ ለአፉየ ።
ወማዕፆ ፡ ዘዐቅም ፡ ለከናፍርየ ።
፬ ኢትሚጦ ፡ ለልብየ ፡ ውስተ ፡ ነገር ፡ እኩይ ።
ለአመክንዮ ፡ ምክንያት ፡ ለኀጢአት ።
ምስለ ፡ ሰብእ ፡ ገበርተ ፡ ዐመፃ ።
ወኢይትኃበር ፡ ምስለ ፡ ኅሩያኒሆሙ ።

፭ ገሥጸኒ ፡ በጽድቅ ፡ ወተዛለፈኒ ፡ በምሕረት ።
ወቅብዐ ፡ ኃጥአንሰ ፡ ኢይትቀባዕ ፡ ርእስየ ።
እስመ ፡ ዓዲ ፡ ጸሎትየኒ ፡ ኢትሣሀሎሙ ።
፮ ተሰጥሙ ፡ በጥቃ ፡ ኰኵሕ ፡ ጽኑዓኒሆሙ ።
ሰምዑኒ ፡ ቃልየ ፡ እስመ ፡ ተክህለኒ ።
፯ ከመ ፡ ግዘፈ ፡ ምድር ፡ ተሰጥቁ ፡ በዲበ ፡ ምድር ።
ወተዘርወ ፡ አዕፅምቲሆሙ ፡ በኀበ ፡ ሲኦል ።
፰ እስመ ፡ ኀቤከ ፡ እግዚኦ ፡ አዕይንትየ ።
ብከ ፡ ተወከልኩ ፡ ኢታውዕአ ፡ ለነፍስየ ።
፱ ዕቀበኒ ፡ እመሥገርት ፡ እንተ ፡ ኀብኡ ፡ ሊተ ።
ወእማዕቅፎሙ ፡ ለገበርተ ፡ ዐመፃ ።
ለይደቁ ፡ ውስተ ፡ መሥገርቶሙ ፡ ኃጥአን ።
፲ እስከ ፡ አኀልፍ ፡ አነ ፡ ባሕቲትየ ።

መዝሙር ፡ ፻፵፩ ።
በእንተ ትሩፋን ።

፩ ቃልየ ፡ ኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸራሕኩ ።
ቃልየ ፡ ኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሰአልኩ ።
፪ ወእከዑ ፡ ቅድሜሁ ፡ ስእለትየ ።
ወእነግር ፡ ቅድሜሁ ፡ ሕማምየ ።
፫ ሶበ ፡ ተኀልቅ ፡ ነፍስየ ፡ በላዕሌየ ።
አንተ ፡ እግዚኦ ፡ ተአምር ፡ ፍኖትየ ።
በዛቲ ፡ ፍኖት ፡ እንተ ፡ ሖርኩ ፡ ኀብኡ ፡ ሊተ ፡ መሥገርተ ።
፬ ወተመየጥኩ ፡ መንገለ ፡ የማንየ ፡ ወርኢኩ ።
ወኀጣእኩ ፡ ዘየአምረኒ ።
ወኀበሂ ፡ አመስጥ ፡ አልብየ ።
ወአልቦ ፡ ዘይትኃሠሥ ፡ በእንተ ፡ ነፍስየ ።
፭ ኀቤከ ፡ እግዚኦ ፡ ጸራሕኩ ፡ ወዕቤለከ ፡ አንተ ፡ ተስፋየ
ወአንተ ፡ መክፈልትየ ፡ በምድረ ፡ ሕያዋን ።



በመንገድ ፡ እንቅፋትን ፡ አኖሩ ።
እግዚአብሔርንም ፡ አንተ ፡ አምላኪ ፡ ነህ ፡ ፮
የልመናዬን ፡ ቃል ፡ አቤቱ ፡ አድምጥ ፡ አልሁት ።
አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ የመድኃኒቴ ፡ ኅልበት ፡ ፯
በሰልፍ ፡ ቀን ፡ ራሴን ፡ ሸፈንህ ።
አቤቱ ፡ ለኀጢአተኞች ፡ ምኞት ፡ አትስጠኝ ፡ ፰
በላዬ ፡ ተማከሩ ፡ እንዳይኰሩ ፡ አትተወኝ ።
የሚከበኙኝን ፡ ራስ ፡ የከንፈራቸው ፡ ክፋት፡ ይክደናቸው ፱
የእሳት ፡ፍም ፡ በላያቸው ፡ ይውደቅ ፤ ፲
እንዳይነሡም ፡ ወደ ፡ እሳትና ፡ ወደ ፡ ማዕበል ፡ ይጣሉ ።
ተናጋሪ ፡ ሰው ፡ በምድር ፡ ውስጥ ፡ አይጸናም ፡ ፲፩
ዓመፀኛን ፡ ሰው ፡ ክፋት ፡ ለጥፋት ፡ ይፈልገዋል ።
እግዚአብሔር ፡ ለችግረኛ ፡ ፍርድን ፡ ፲፪
ለድኃም ፡ በቀልን ፡ እንዲያደርግ ፡ አወቅሁ ።
ጻድቃንም ፡ በእውነት፡ስምህን ፡ ያመሰግናሉ ፡ ፲፫
ቅኖችም ፡ በፊትህ ፡ ይኖራሉ ።

መዝሙር ፡ ፻፵ ።

ስለ ትሩፋን ።

አቤቱ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ጮኽሁ ፡ ፩
ወደ ፡ አንተ ፡ ስጮኽም ፡ የልመናዬን ፡ ቃል ፡ አድምጥ ።
ጸሎቴን ፡ በፊትህ ፡ እንደ፡ዕጣን ፡ ተቀበልልኝ ፡ ፪
እጅ ፡ መንሣቴም ፡ እንደ ፡ ሠርክ ፡ መሥዋዕት ፡ ትሁን ።
አቤቱ ፡ ለአፌ ፡ ጠባቂ ፡ አኑር ፡ ፫
የከንፈሮቼንም ፡ መዝጊያ ፡ ጠብቅ ።
ልቤን ፡ ወደ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አትመልሰው ፡ ፬
ዓመፅን ፡ ከሚያደርጉ ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ አትደምረኝ ።
ለኃጢአት ፡ ምክንያት ፡ እንዳልሰጥ ፡
ከምርጦቻቸውም ፡ ጋራ ፡ አልተባበር ።

ጻድቅ ፡ በምሕረት ፡ ይገሥጸኝ ፡ ይዝለፈኝም ፡ ፭
የኃጢአተኛ ፡ ዘይት ፡ ግን ፡ እራሴን ፡ አይቅባ ፡
ጸሎቴ ፡ ገና ፡ በክፋታቸው ፡ ላይ ፡ ነው ።
ኃይለኞቻቸው ፡ በጭንጫ ፡ አጠገብ ፡ ተጣሉ ፡ ፮
ጣፋጭ ፡ ናትና ፡ ነገሬን ፡ ይሰማሉ ።
በምድር ላይ እንደ ተሠነጠቀ እንደ መሬት ስብ ፤ ፯
እንዲሁ ፡ አጥንቶቻችን ፡ በሲኦል ፡ ተበተኑ ።
አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ ዓይኖቼ ፡ወደ ፡ አንተ ፡ ናቸውና ፡ ፰
በአንተ ፡ ታመንሁ ፡ ነፍሴን ፡ አታውጣት ።
ዓመፅን ፡ ከሚያደርጉ ፡ ወጥመድ ፡ ፱
ከሰወሩብኝም ፡ እንቅፋት ፡ ጠብቀኝ ።
እኔ ፡ ብቻዬን ፡ እስካልፍ ፡ ድረስ ፡ ፲
ኃጢአተኞች ፡ በወጥመዳቸው ፡ ይውደቁ ።

መዝሙር ፡ ፻፵፩ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

በቃሌ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኽሁ ፤ ፩
በቃሌ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለመንሁ ።
ልመናዬን ፡ በፊቱ ፡ አፈሳለሁ ፡ ፪
መከራዬንም ፡ በፊቱ ፡ እናገራለሁ ።
ነፍሴ ፡ በውስጤ ፡ ባለቀች ፡ ጊዜ ፡ መንገዴን ፡ አወቅሁ ፡ ፫
በምሄድባት ፡ በዚያች ፡ መንገድ፡ ወጥመድን ፡ ሠወሩብኝ።
ወደ ፡ ቀኝ ፡ ተመለከትሁ ፡ አየሁም ፡ ፬
የሚያውቀኝም ፡ የለም ፤ መሸሸጊያም ፡ አጣሁ ፤
ስለ ፡ ነፍሴም ፡ የሚመራመር ፡ የለም ፡
አቤቱ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ጮኽሁ ፡ ፭
አንተ ፡ ተስፋዬ ፡ ነህ ፤
በሕያዋንም ፡ ምድር ፡ አንተ ፡ ፈንታዬ ፡ ነህ ፡ አልሁ ።

፮ ነጽር ፡ ስእለትየ ፡ እስመ ፡ ሐመምኩ ፡ ፈድፋደ ።
አድኅንኒ ፡ እምእለ ፡ ሮዱኒ ፡ እስመ ፡ ይኄይሉኒ ።
ወአውፅአ ፡ እሞቅህ ፡ ለነፍስየ ።
፯ ከመ ፡ እግነይ ፡ ለስምከ ፡ እግዚአ ።
ኪያየ ፡ ይጸንሑ ፡ ጻድቃን ፡ እስከ ፡ ሶበ ፡ ተዐስየኒ ።

መዝሙር ፡ ፻፵፪ ።

በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ እግዚአ ፡ ስምዐኒ ፡ ጸሎትየ ።
ወአጽምዐኒ ፡ ስእለትየ ፡ በጽድቅከ ።
ወስምዐኒ ፡ በርትዕከ ።
ወኢትባእ ፡ ውስተ ፡ ቅሥት ፡ ምስለ ፡ ገብርከ ።
፪ እስመ ፡ ኢይጸድቅ ፡ ኵሉ ፡ሕያው ፡ በቅድሜከ ።
፫ እስመ ፡ ሮዳ ፡ ጸላኢ ፡ ለነፍስየ ።
ወአሕሠራ ፡ ውስተ ፡ ምድር ፡ ለሕይወትየ ።
ወአንበሩኒ ፡ ውስተ ፡ ጽልመት ፡ ከመ ፡ ምዉተ ፡ ትካት
፬ ወቀብጸተኒ ፡ ነፍስየ ፡ በላዕሌየ ።
ወደንገጸኒ ፡ ልብየ ፡ በውስጥየ ።
፭ ወተዘከርኩ ፡ መዋዕለ ፡ ትካት ።
ወአንበብኩ ፡ በኵሉ ፡ ግብርከ ።
ወአነብብ ፡ ግብረ ፡ እደዊከ ።
፮ ወአንቃእኩ ፡ እደውየ ፡ ኀቤከ ።
ነፍስየኒ ፡ ከመ ፡ ምድረ ፡ በድው ፡ ጸምአተከ ።
፯ ፍጡነ ፡ ስምዐኒ ፡ እግዚአ ፡ ኀለፈት ፡ ነፍስየ ።
ወኢትሚጥ ፡ ገጸከ ፡ እምኔየ ።
ወኢይኩን ፡ ከመ ፡ እለ ፡ ይወርዱ ፡ ውስተ ፡ ዐዘቅት ።
ዘይሰማዕ ፡ ግበር ፡ ሊተ ፡ ምሕረተከ ፡ በጽባሕ ።
፰ እስመ ፡ ኪያከ ፡ ተወከልኩ ፡ እግዚአ ።
ምርሐኒ ፡ እግዚኦ ፡ ፍኖተ ፡ እንተ ፡ ባቲ ፡ አሐውር ።
እስመ ፡ ኀቤከ ፡ አንቃዕዱኩ ፡ ነፍስየ ።
፱ አድኅነኒ ፡ እግዚአ ፡ እምፀርየ ።
እስመ ፡ ኀቤከ ፡ ተማኅፀንኩ ።
፲ ምሀረኒ እግዚአ ለገቢረ ፈቃድከ እስመ አምላኪየ አንተ
ወመንፈስከ ፡ ቅዱስ ፡ ይምርሐኒ ፡ በምድረ ፡ ጽድቅ ።
፲፩ በእንተ ፡ ስምከ ፡ እግዚአ ፡ አሕይወኒ ፡ በጽድቅከ ።
ወአውፅአ ፡ እምንዳቤሃ ፡ ለነፍስየ ።
፲፪ ወበሥምረትከ ፡ ሠርዎሙ ፡ ለፀርየ ።
ወታጠፍእሙ ፡ ለኵሎሙ ፡ እለ ፡ የሐምምዋ ፡ ለነፍስየ ።
እስመ ፡ አነ ፡ ገብርከ ።

መዝሙር ፡ ፻፵፫ ።

በእንተ ፡ ርእሱ ፡ ወበእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ ይትባረክ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላኪየ ።
ዘመሀሮን ፡ ጸብአ ፡ ለእደውየ ። ወቀትለ ፡ ለአጻብዕየ ።
፪ መሀርየ ፡ ወፀወንየ ። ምስካይየ ፡ ወመድኀኒየ ።
ምእመንየ ፡ ወኪያሁ ፡ ተወከልኩ ።
ዘያገርር ፡ ሊተ ፡ አሕዛበ ፡ በመትሕቴየ ።
፫ እግዚኦ ፡ ምንትኑ ፡ ውእቱ ፡ ሰብእ ፡ ከመ፡ ታስተርኢ ፡ሎቱ ።
ዕጓለ ፡ እመሕያውስ ፡ ዘተሐስቦ ።
፬ ሰብእሰ ፡ ከንቶ ፡ ይመስል ።
ወመዋዕሊሁኒ ፡ ከመ ፡ ጽላሎት ፡ የኀልፍ ።
፭ እግዚአ ፡ አጽንን ፡ ሰማያቲከ ፡ ወረድ ።
ግሥሦሙ ፡ ለአድባር ፡ ወይጠይሱ ።
፮ አብርቅ ፡ መባርቅቲከ ፡ ወዝርዎሙ ።
ፈኑ ፡ አሕጻከ ፡ ወሁኮሙ ።
፯ ፈኑ ፡ እዴከ ፡ እምአርያም ።
አድኅነኒ ፡ ወባልሐኒ ፡ እማይ ፡ ብዙኅ ።
ወእምእዴሆሙ ፡ ለደቂቀ ፡ነኪር ።
እለ ፡ ከንቶ ፡ ነበበ ፡ አፉሆሙ ።



እጅግ ፡ ተቸግሬአለሁና ፡ ወደ ፡ ልመናዬ ፡ አድምጥ ፡ ፮
በርትተውብኛልና ፡ ከሚያሳድዱኝ ፡ አድነኝ ።
አቤቱ ፡ ስምህን ፡ አመሰግን ፡ ዘንድ ፡ ፯
ነፍሴን ፡ ከወህኒ ፡ አውጣት ፡
ዋጋዬን፡ እ ስክትሰጠኝ ፡ ድረስ ፤
ጻድቃን ፡ እኔን ፡ ይጠብቃሉ ።

መዝሙር ፡ ፻፵፪ ።

ስለትሩፋን ።

አቤቱ ፡ ጸሎቴን ፡ ስማ ፡ ፩
በውነትህ ፡ ልመናዬን ፡ አድምጥ ፡
በጽድቅህም ፡ መልስልኝ ።
ሕያው ፡ ሁሉ ፡ በፊትህ ፡ ጻድቅ ፡ አይደለምና ፡ ፪
ከባሪያህ ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ ፍርድ ፡ አትግባ ።
ጠላት ፡ ነፍሴን ፡ አሳዶአታል ፡ ፫
ሕይወቴንም ፡ በምድር ፡ ውስጥ ፡ አጕስቍሏታል ፡
ቀድሞ ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ ሰው ፡ በጨለማ ፡ አኑሮኛል ።
ነፍሴ ፡ በውስጤ ፡ አለቀችብኝ ፡ ፬
ልቤም ፡ በውስጤ ፡ ደነገጠብኝ ።
የቀድሞውን ፡ ዘመን ፡ አሰብሁ ፡ ፭
ሥራህንም ፡ ሁሉ ፡ ተመለከትሁ ፡
የእጅህንም ፡ ሥራ ፡ አስተዋልሁ ።
እጆቼን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ዘረጋሁ ፡ ፮
ነፍሴም ፡ እንደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ አንተን ፡ ተጠማች ፡
አቤቱ ፡ ፈጥነህ ፡ ስማኝ ፡ ነፍሴ ፡ አልቃለች ፡ ፯
ፊትህን ፡ ከኔ ፡ አትመልስ ።
ወደ ፡ ጕድጓድም ፡ እንደሚወርዱ ፡ አልሁን ፤
አንተን ፡ ታምኜአለሁና ፡ ፰
በማለዳ ፡ ምሕረትህን ፡ አሰማኝ ፤
አቤቱ ፡ ነፍሴን ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ አንሥቻለሁና ፡
የምሄድበትን ፡ መንገድ ፡ አስታውቀኝ ።
አቤቱ ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ ተማጽኜአለሁና ፡ ፱
ከጠላቶቼ ፡ አድነኝ ።
አንተ፡አምላኬ፡ነህና፡ፈቃድህን፡ለማድረግ፡አስተምረኝ፡ ፲
ቅዱስ ፡ መንፈስህም ፡ በጽድቅ ፡ ምድር ፡ ይምራኝ ።
አቤቱ ፡ ስለ ፡ ስምህ ፡ በጽድቅ ፡ ሕያው ፡ አድርገኝ ፡ ፲፩
ነፍሴንም ፡ ከመከራዋ ፡ አውጣት ።
በምሕረትህ ፡ ጠላቶቼን ፡ ደምስሳቸው ፡ ፲፪
እኔ ፡ ባሪያህ ፡ ነኝና ፡
ነፍሴን ፡ የሚያስጨንቋትን ፡ ሁሉ ፡ አጥፋቸው ።

መዝሙር ፡ ፻፵፫ ።

ስለራሱና ፡ ስለትሩፋን ።

እግዚአብሔር ፡ አምላኬ ፡ ይባረክ ፡ ፩
ለእጆቼ ፡ ሰልፍን ፡ ለጣቶቼም ፡ ተዋስን ፡ የሚያስተምር ።
መሐሪዬ ፡ መሸሸጊያዬ ፡ መጠጊያዬ ፡ መድኀኒቴ ፡ ፪
ረዳቴም ፡ መታመኛዬም ፡
ሕዝቤንም ፡ ከእኔ ፡ በታች ፡ የሚያስገዛልኝ ።
አቤቱ፡ እርሱን፡ ታውቀው፡ ዘንድ፡ ሰው፡ ምንድር፡ ነው ? ፫
ታስበለት ፡ ዘንድ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ምንድር ፡ ነው ።
ሰው ፡ ከንቱን ፡ ነገር ፡ ይመስላል ፡ ፬
ዘመኑ ፡ እንደ ፡ ጥላ ፡ ያልፋል ።
አቤቱ፡ ሰማዮችህን፡ ዝቅ፡ዝቅ፡ አድርጋቸው፡ ውረድም ፡ ፭
ተራሮችን ፡ ዳሳቸው ፡ ይጢሱም ።
መባርቅቶችህን ፡ ብልጭ፡ አድርጋቸው፡ በትናቸውም ፡ ፮
ፍላጾችህን ፡ ላካቸው ፡ አስደንግጣቸውም ።
እጅህን ፡ ከአርያም ፡ ላክ ፡ አድነኝም ፡ ፯
ከብዙ ፡ ውኆች ፡ አፋቸውም ፡ ምናምንን ፡ ከሚናገር ፡

፰ ወየማኖሙኒ ፡ የማነ ፡ ዐመፃ ።
፱ እግዚኦ ፡ ስብሐተ ፡ ሐዲሰ ፡ እሴብሐከ ።
መበመዝሙር ፡ ዘዐሠርቱ ፡ አውታሪሁ ፡ እዜምር ፡ ለከ ።
፲ ዘይሁቦሙ ፡ ለነገሥት ፡ መድኃኒተ ።
ዘአድኅኖ ፡ ለዳዊት ፡ ገብሩ ፡ እምኲናት ፡ እኪት ።
፲፩ አድኅነኒ ፡ ወባልሐኒ ፡ እምእዴሆሙ ፡ ለደቂቀ ፡ ነኪር ።
እለ ፡ ከንቶ ፡ ነበበ ፡ አፉሆሙ ።
ወየማኖሙኒ ፡ የማነ ፡ ዐመፃ ።
፲፪ እለ ፡ ደቂቆሙ ፡ ከመ ፡ ተክለ ፡ ዘይት ፡ ሐዲስ ፡
ጽኑዓን ፡ በውርዙቶሙ ።
ወአዋልዲሆሙኒ ፡ ርሱያት ።
ወሥርግዋት ፡ ከመ ፡ እንተ ፡ ጽርሕ ።
፲፫ ወአብያቲሆሙኒ ፡ ምሉዕ ።
ወይሰወጥ ፡ እምዝ ፡ ውስተዝ ።
ወአባግዒሆሙኒ ፡ ብዙኃን ፡ ይትዋለዱ ።
ወይትባዝኃ ፡ በሙፋሪሆን ።
፲፬ ወአልህምቲሆሙኒ ፡ ሥቡሕ ።
ወአልቦ ፡ ድቀት ፡ ለቅጽሮሙ ።
ወአልቦ ፡ እንተ ፡ ኀበ ፡ ይበውእዎሙ ።
ወአልቦ ፡ ዐውያት ፡ ውስተ ፡ ሀገሮሙ ።
፲፭ አስተብፅዕዎ ፡ ለዘከመዝ ፡ ሕዝብ ።
ብፁዕ ፡ ሕዝብ ፡ ዘእግዚአብሔር ፡ አምላኩ ።

መዝሙር ፡ ፻፵፬ ።

በእንተ ፡ ርእሱ ፡ ወበእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ አሌዕለከ ፡ ንጉሥየ ፡ ወአምላኪየ ።
ወእባርከ ፡ ለስምከ ።
ለዓለም ፡ ወለዓለመ ፡ ዓለም ።
፪ ኵሎ ፡ አሚረ ፡ እባርከከ ። ወእሴብሕ ፡ ለስምከ ።
ለዓለም ፡ ወለዓለመ ፡ ዓለም ።
፫ ዐቢይ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወብዙኅ ፡ አኰቴቱ ።
ወአልቦ ፡ ጽንፍ ፡ ለዕበየ ፡ ዚአሁ ።
፬ ትውልደ ፡ ትውልድ ፡ ይንዕዱ ፡ ምግባሪከ ።
ወይዜንዉ ፡ ኀይለከ ።
፭ ወይነግሩ ፡ ዕበየ ፡ ክብረ ፡ ስብሐተ ፡ ቅድሳቲከ ።
ወያየድዑ ፡ መንክረከ ።
፮ ወይብሉ ፡ ግሩም ፡ ኃይልከ ።
ወይነግሩ ፡ ኀይለ ፡ ግርማከ ።
ወያየድዑ ፡ ጽንዐከ ።
፯ ወይጐሥዑ ፡ ተዝካረ ፡ ብዝኀ ፡ ምሕረትከ ።
ወይትሐሠዩ ፡ በጽድቅከ ።
፰ መሐሪ ፡ ወመስተሣህል ፡ እግዚአብሔር ።
ርኁቀ ፡ መዓት ፡ ወብዙኀ ፡ ምሕረት ፤ ወጻድቅ ።
፱ ኄር ፡ እግዚአብሔር ፡ ለኵሉ ፡ ይትዔገሥዎ ።
ወሣህሉ ፡ ላዕለ ፡ ኵሉ ፡ ተግባሩ ።
፲ ይገንዩ ፡ ለከ ፡ እግዚኦ ፡ ኵሉ ፡ ተግባርከ ።
ይባርኩከ ፡ ጻድቃኒከ ።
፲፩ ስብሐተ ፡ ይብሉ ፡ ለመንግሥትከ። ወይነግሩ፡ ኃይለከ
ከመ ፡ ይንግርዎሙ ፡ ለዕጓለ ፡ እመሕያው ፡ ኀይለከ ።
፲፪ ወዕበየ ፡ ክብረ ፡ ስብሐተ ፡ መንግሥትከ ።
፲፫ መንግሥትከሰ ፡ መንግሥት ፡ ዘለኵሉ ፡ ዓለም ።
ወምኵናኒከኒ ፡ ለትውልደ ፡ ትውልድ ።
፲፬ ምእመን ፡ እግዚአብሔር ፡ በኵሉ ፡ ቃሉ ።
ወጻድቅ ፡ በኵሉ ፡ ምግባሩ ።
ይሰውቆሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለእለ ፡ ተንተኑ ።
ያነሥኦሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለእለ ፡ ወድቁ ።
፲፭ ዓይነ ፡ ኵሉ ፡ ነፍስ ፡ ይሴፎ ፡ ኪያከ ።
አንተ ፡ ትሁቦሙ ፡ሲሳዮሙ ፡ በጊዜሁ ።
፲፮ ትሰፍሕ ፡ የማነከ ፤ ወታጸግብ ፡ ለኵሉ ፡ እንስሳ ፡
ዘበሥርዐትከ ።



ቀኛቸው ፡ የሐሰት ፡ ቀኝ ፡ ከሆነ ፡ ፰
ከባዕድ ፡ ልጆች ፡ እጅ ፡ አስጥለኝ ።
አቤቱ ፡ አዲስ ፡ ቅኔ ፡ እቀኝልሃለሁ ፡ ፱
ዓሥር ፡ አውታር ፡ ባለው ፡ በገና ፡ እዘምርልሃለሁ ።
ለነገሥታት ፡ መድኃኒትን ፡ የሚሰጥ ፡ ፲
ባሪያውን ፡ ዳዊትን ፡ ከክፉ ፡ ሰይፍ ፡ የሚያድነው ፡
እርሱ ፡ ነው ።
አድነኝ፡ አፋቸውም፡ ምናምንን ፡ ከሚናገር ፡ ፲፩
ቀኛቸውም ፡ የሐሰት ፡ ቀኝ ፡ ከሆነ ፡
ከባዕድ ፡ ልጆች ፡ እጅ ፡ አስጥለኝ ።
ልጆቻቸው ፡ በጕልማስነታቸው ፡ እንደ ፡ አዲስ ፡ ፲፪
አትክልት ፡ የሆኑ ፡
ሴቶች ፡ ልጆቻቸውም ፡ እንደ፡ እልፍኝ፡ ያማሩና፡ያጌጡ ፡
ግምጃ ፡ ቤቶቻቸውም ፡ በያይነቱ ፡ ዕቃን ፡ የተሞሉ ፡ ፲፫
በጎቻቸውም ፡ ብዙ ፡ የሚወልዱ ።
በመሠማሪያቸውም ፡ የሚበዙ ፡
ላሞቻቸውም ፡ የሚወፍሩ ፡ ፲፬
ቅጥራቸውም ፡ መፍረሻና ፡ መውጫ ፡ የሌለው ፡
በአደባባዮቻቸውም ፡ ዋይታ ፡ የሌለ ።
እንደዚህ ፡ የሚሆን ፡ ሕዝብ ፡ የተመሰገነ ፡ ነው ፡ ፲፭
እግዚአብሔር ፡ አምላኩ ፡ የሆነ ፡ ሕዝብ፡ምስጉን፡ነው ።

መዝሙር ፡ ፻፵፬ ።

ስለራሱና ፡ ስለትሩፋን ።

አምላኬ ፡ ንጉሤ ፡ ሆይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደርግሃለሁ ፡ ፩
ስምህንም ፡ ለዘላለም ፡ ዓለምም ፡ አባርካለሁ ።
በየቀኑ ፡ ሁሉ ፡ እባርክሃለሁ ፡ ፪
ስምህንም ፡ ለዘላለም ፡ ዓለምም ፡ አመሰግናለሁ ።
እግዚአብሔር ፡ ታላቅ፡ ነው፡ እጅግም፡የተመሰገነ፡ ነው ፡ ፫
ለታላቅነቱም ፡ ፍጻሜ ፡ የለውም ።
ልጅ ፡ የልጅ ፡ ልጅ ፡ ሥራህን ፡ ያመሰግናሉ ፡ ፬
ኃይልህንም ፡ ያወራሉ ።
የቅድስናህን ፡ ግርማ ፡ ክብር ፡ ይናገራሉ ፡ ፭
ተአምራትህንም ፡ ይነጋገራሉ ።
የግርማህንም ፡ ኀይል ፡ ይናገራሉ ፡ ፮
ታላቅነትህንም ፡ ይናጋገራሉ ፡
ብርታትህንም ፡ ይነጋገራሉ ።
የቸርነትህን ፡ ብዛት ፡ መታሰብ ፡ ያወጣሉ ፡ ፯
በጽድቅህም ፡ ሐሤትን ፡ ያደርጋሉ ።
እግዚአብሔር ፡ ርኅሩኅና ፡ መሓሪ ፡ ነው ፡ ፰
ከቍጣ ፡ የራቀ ፡ ምሕረቱም ፡ የበዛ ፡ ነው ።
እግዚአብሔር ፡ ለትዕግሥተኞች ፡ ቸር ፡ ነው ፡ ፱
ምሕረቱም ፡ በሥራው ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ነው ።
አቤቱ ፡ ሥራዎችህ ፡ ሁሉ ፡ ያመሰግኑሃል ፡ ፲
ቅዱሳንህም ፡ ይባርኩሃል ።
ለሰው ፡ ልጆች ፡ ኃይልህን ፡ ፲፩
የመንግሥትህንም ፡ ግርማ ፡ ክብር ፡ ያስታውቁ፡ዘንድ ።
የመንግሥትህን ክብር ይናገራሉ ኃይልህንም ይነጋገራሉ ። ፲፪
መንግሥትህ ፡ የዘላለም ፡ መንግሥት ፡ ናት ። ፲፫
ግዛትህም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ነው ።
እግዚአብሔር ፡ በቃሎቹ ፡ የታመነ ፡ ነው ፡ ፲፬
በሥራውም ፡ ሁሉ ፡ ጻድቅ ፡ ነው ።
እግዚአብሔር ፡ የተፍገመገሙትን፡ሁሉ፡ይደግፋቸዋል፤
የወደቁትንም ፡ ያነሣቸዋል ።
የሁሉ ፡ ዓይን ፡ አንተን ፡ ተስፋ ፡ ያደርጋል ፡ ፲፭
አንተም ፡ ምግባቸውን ፡ በየጊዜው ፡ ትሰጣቸዋለህ ።
አንተ ፡ እጅህን ፡ ትዘረጋለህ ፡ ፲፮
ለሕያውም ፡ ሁሉ ፡ መልካሙን ፡ ታጠግባለህ ።

፲፯ ጻድቅ እግዚአብሔር ፡ በኵሉ ፡ ፍናዊሁ ።
ወኄር ፡ በኵሉ ፡ ምግባሩ ።
፲፰ ቅሩብ ፡ እግዚአብሔር ለኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይጼውዕዎ።
ወለኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይጼውዕዎ ፡ በጽድቅ ።
፲፱ ይገብር ፡ ፈቃዶሙ ፡ ለእለ ፡ ይፈርህዎ ።
ይሰምዖሙ ፡ ጸሎቶሙ ፡ ወያድኅኖሙ ።
፳ የዐቅቦሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይፈርህዎ ።
ወይሤርዎሙ ፡ ለኵሎሙ ፡ ኃጥአን ።
፳፩ ስብሐተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይነግር ፡ አፉየ ።
ወኵሉ ፡ ዘሥጋ ፡ ይባርክ ፡ ለስሙ ፡ ቅዱስ ።
ለዓለም ፡ ወለዓለመ ፡ ዓለም ።

መዝሙር ፡ ፻፵፭ ።
በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ ሃሌ ፡ ሉያ ፤
ተአኵቶ ፡ ነፍስየ ። ለእግዚአብሔር ።
፪ እሴብሖ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በሕይወትየ ።
ወእዜምር ፡ ለአምላኪየ ፡ በአምጣነ ፡ ሀሎኩ ።
ኢትትአመኑ ፡ በመላእክት ።
፫ ወኢበዕጓለ ፡ እመሕያው ፡ እለ ፡ ኢይክሉ ፡ አድኅኖ ።
፬ ትወፅእ ፡ ነፍሶሙ ፡ ወይገብኡ ፡ ውስተ ፡ መሬቶሙ ።
ውእተ ፡ አሚረ ፡ ይጠፍእ ፡ ኵሉ ምክሮሙ
፭ ብፁዕ ፡ ብእሲ ፡ ዘአምላከ ፡ ያዕቆብ ፡ ረዳኢሁ ።
ወትውክልቱኒ ፡ ላዕለ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላኩ ።
ዘገብረ ፡ ሰማየ ፡ ወምድረ ።
ወባሕረ ፡ ወኵሎ ፡ ዘውስቴታ ።
፮ ዘየዐቅባ ፡ ለጽድቅ ፡ ዘለዓለም ።
ወይፈትሕ ፡ ሎሙ ፡ ለግፉዓን ።
፯ ዘይሁቦሙ ፡ ሲሳዮሙ ፡ ለርኁባን ።

፰ እግዚአብሔር ፡ ይፈትሖሙ ፡ ለሙቁሓን ።
እግዚአብሔር ፡ ያነሥኦሙ ፡ ለእለ ፡ ወድቁ ።
፱ እግዚአብሔር ፡ ያጠብቦሙ ፡ ለዕዉራን ።
እግዚአብሔር ፡ ያፈቅሮሙ ፡ ለጻድቃን ።
እግዚአብሔር ፡ የዐቅቦሙ ፡ ለፈላስያን ።
ወይትዌከፎሙ ፡ ለዕቤራት ፡ ወለዕጓለ ፡ ማውታ ።
ወያማስኖ ፡ ፍኖተ ፡ ኃጥአን ።
፲ ይነግሥ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ።
አምላክኪ ፡ ጽዮን ፡ ለትውልደ ፡ ትውልድ ።

መዝሙር ፡ ፻፵፮ ።
በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ ሰብሕዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እስመ፡ሠናይ፡መዝሙር ።
ወለአምላክነ ፡ ሐዋዝ ፡ ሰብሖ ።
፪ የሐንጻ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለኢየሩሳሌም ።
ወያስተጋብእ ፡ ዝርወቶሙ ፡ ለእስራኤል ።
፫ ዘይፌውሶሙ ፡ ለቍሱላነ ፡ ልብ ።
ወያጸምም ፡ ሎሙ ፡ ቍስሎሙ ።
፬ ዘይኌልቆሙ ፡ ለከዋክብት ፡ በምልዖሙ ።
ወይጼውዖሙ ፡ ለኵሎሙ ፡ በበአስማቲሆሙ
፭ ዐቢይ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወዐቢይ ፡ ኀይሉ ።
ወአልቦ ፡ ኍልቍ ፡ ለጥበቢሁ ።
፮ ያነሥኦሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለየዋሃን ።
ወያኀስሮሙ ፡ ለኃጥአን ፡ እስከ ፡ ምድር ።
፯ ሰብሕዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በአሚን ።
ወዘምሩ ፡ ለአምላክነ ፡ በመሰንቆ ።
፰ ዘይገለብቦ ፡ ለሰማይ ፡ በደመና ።
ወያስተዴሉ ፡ ክረምተ ፡ ለምድር ።
ዘያበቍል ፡ ሣዕረ ፡ ውስተ ፡ አድባር ።



እግዚአብሔር ፡ በመንገዱ ፡ ሁሉ ፡ ጻድቅ ፡ ነው ፤ ፲፯
በሥራውም ፡ ሁሉ ፡ ቸር ፡ ነው ።
እግዚአብሔር ፡ ለሚጠሩት ፡ ሁሉ ፤ ፲፰
በእውነት ፡ ለሚጠሩት ፡ ሁሉ ፡ ቅርብ ፡ ነው ።
ለሚፈሩት ፡ ምኞታቸውን ፡ ያደርጋል ፤ ፲፱
ልመናቸውንም ፡ ይሰማል ፡ ያድናቸዋልም ።
እግዚአብሔር ፡ የሚወዱትን ፡ ሁሉ ፡ ይጠብቃል ፤ ፳
ኃጢአተኞችንም ፡ ሁሉ ፡ ያጠፋል ።
አፌ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ምስጋና ፡ ይናገራል ፤ ፳፩
ሥጋም ፡ ሁሉ ፡ ለዘላለም ፡ ዓለም ፡ የተቀደሰውን ፤
ስሙን ፡ ይባርክ ።

መዝሙር ፡ ፻፵፭ ።
ስለ ትሩፋን ።

ሃሌ ፡ ሉያ ፤
ነፍሴ ፡ ሆይ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኚ ። ፩
በሕይወቴ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰግናለሁ ፤ ፪
በምኖርበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ለአምላኬ ፡ እዘምራለሁ ።
ማዳን ፡ በማይችሉ ፡ በሰው ፡ ልጆችና ፡ በአለቆች ፤ ፫
አትታመኑ ።
ነፍሱ ፡ ትወጣለች ፡ ወደ፡መሬትነቱም ፡ ይመለሳል ፤ ፬
ያን ፡ ጊዜ ፡ ምክሩ ፡ ሁሉ ፡ ይጠፋል ።
የያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ ረዳቱ ፡ የሆነ ፤ ፭
ተስፋው ፡ ሰማይንና ፡ ምድርን ፡ ባሕርን ፡ በእነርሱ ፤
ያለውንም ፡ ሁሉ ፡ በፈጠረ ።
እውነትን ፡ ለዘላለም ፡ የሚጠብቅ ፤ ፮
ለተበደሉት ፡ በሚፈርድ ።
ለተራቡም ፡ ምግብን ፡ በሚሰጥ ፤ ፯

በአምላኩ፡ በእግዚአብሔር ፡ የሆነ፡ ሰው፡ ምስጉን፡ ነው ።
እግዚአብሔር ፡ የታሠሩትን ፡ ይፈታል ።
እግዚአብሔር ፡ የወደቁትን ፡ ያነሣል ፤
እግዚአብሔር ፡ ዕውሮችን ፡ ብልሆች ፡ ያደርጋቸዋል ። ፰
እግዚአብሔር ፡ ጻድቃንን ፡ ይወዳል ፤
እግዚአብሔር ፡ ስደተኞችን ፡ ይጠብቃል ። ፱
ድሀ ፡ አደጎችንና ፡ ባልቴቶችን ፡ ይቀበላል ፤ ፲
የኃጢአተኞችንም ፡ መንገድ ፡ ይዘጋል ።
እግዚአብሔር ፡ ለዘላለም ፡ ይነግሣል ፤ ፲፩
ጽዮን ፡ ሆይ ፡ አምላክሽ ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ነው ።
ሃሌ ፡ ሉያ ።

መዝሙር ፡ ፻፵፮ ።
ስለትሩፋን ።

እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑ፡ መዝሙር ፡ መልካም፡ነውና፡ ፩
ለአምላካችን ፡ ምስጋና ፡ ያማረ ፡ ነው ።
እግዚአብሔር ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ ይሠራል ፤ ፪
ከእስራኤልም ፡ የተበተኑትን ፡ ይሰበስባል ።
ልባቸው ፡ የቆሰለውን ፡ ይፈውሳል፤ ፫
ሕማማቸውንም ፡ ይጠግናል ።
የከዋክብትንም ፡ ብዛት ፡ ይቈጥራል ፤ ፬
ሁሉንም ፡ በየስማቸው ፡ ይጠራቸዋል ፤
ጌታችን ፡ ታላቅ፡ነው ፡ ኀይሉም ፡ ታላቅ ፡ ነው ፤ ፭
ለጥበቡም ፡ ቍጥር ፡ የለውም ።
እግዚአብሔር ፡ የዋሃንን ፡ ያነሣል ። ፮
ኃጢአተኞችን ፡ ግን ፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ድረስ ፡ ያዋርዳል ።
ለእግዚአብሔር ፡ በሃይማኖት ፡ ዘምሩ ፤ ፯
ለአምላካችንም ፡ በመሰንቆ ፡ ዘምሩ ።
ሰማዩን በደመናት ይሸፍናል ፤ ለምድርም ዝናምን ያዘጋጃል ። ፰
ሣርንም ፡ በተራሮች ፡ ላይ ፤

ወሐመልማለ ፡ ለቅኔ ፡ ዕጓለ ፡ እመሕያው ።
ዘይሁቦሙ ፡ ሲሳዮሙ ፡ ለእንስሳ ።
፱ ወለዕጕለ ፡ ቋዓት ፡ እለ ፡ ይጼውዕዎ ።
፲ ኢይፈቅድ ፡ ኀይለ ፡ ፈረስ ።
ወኢይሠምር ፡ በአቍያጸ ፡ ብእሲ ።
፲፩ ይሠምር እግዚአብሔር ፡ በእለ ፡ ይፈርህዎ ።
ወበኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይትዌከሉ ፡ በምሕረቱ ።

መዝሙር ፡ ፻፵፯ ።
በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ ትሴብሖ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ለእግዚአብሔር ።
፪ ወሰብሒዮ ፡ ለአምላክኪ ፡ ጽዮን ።
እስመ ፡ አጽንዐ ፡ መናስግተ ፡ ኆኃትኪ ።
ወባረኮሙ ፡ ለውሉድኪ ፡ በውስቴትኪ ።
፫ ወረሰየ ፡ ሰላመ ፡ ለበሐውርትኪ ።
ወአጽገበኪ ፡ ቄቅሐ ፡ ሥርናይ ።
፬ ዘይፌኑ ፡ ቃሎ ፡ ለምድር ።
ወፍጡነ ፡ ይረውጽ ፡ ነቢቡ ።
፭ ዘይሁብ ፡ በረደ ፡ ከመ ፡ ፀምር ።
ወይዘርዎ ፡ ለጊሜ ፡ ከመ ፡ ሐመድ ።
፮ ወያወርድ ፡ በረደ ፡ ከመ ፡ ፍትታት ።
ወመኑ ፡ ይትቃወሞ ፡ ለቍሩ ።
፯ ይፌኑ ፡ ቃሎ ፡ ወይመስዎ ።
ይነፍሕ ፡ መንፈሶ ፡ ወያውኅዝ ፡ ማየተ ።
፰ ዘነገረ ፡ ቃሎ ፡ ለያዕቆብ ።
ፍትሐ ፡ ወኵነኔሁ ፡ ለእስራኤል ።
፱ ወኢገብረ ፡ ከማሁ ፡ ለባዕዳን ፡ አሕዛብ ።
ወኢነገሮሙ ፡ ፍትሐ ።

መዝሙር ፡ ፻፵፰ ።
በእንተ ፡ ትሩፋን ።

ሃሌ ፡ ሉያ ፤
፩ ሰብሕዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እምሰማያት ።
ይሴብሕዎ ፡ በአርያም ።
፪ ይሴብሕዎ ፡ ኵሎሙ ፡ መላእክቲሁ ።
ይሴብሕዎ ፡ ኵሉ ፡ ኀይሉ ።
፫ ይሴብሕዎ ፡ ፀሐይ ፡ ወወርኅ ።
ይሴብሕዎ ፡ ኵሉ ፡ ከዋክብት ፡ ወብርሃን ።
፬ ይሴብሕዎ ፡ ሰማየ ፡ ሰማያት ።
ማይኒ ፡ ዘመልዕልተ ፡ ሰማያት ።
ይሴብሑ ፡ ለስመ ፡ እግዚአብሔር ።
፭ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ይቤ ፡ ወኮኑ ።
ወውእቱ ፡ አዘዘ ፡ ወተፈጥሩ ።
፮ ወአቀሞሙ ፡ ለዓለም ፡ ወለዓለመ ፡ ዓለም ።
ትእዛዘ ፡ ወሀቦሙ ፡ ወኢኀለፉ ።
ሰብሕዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እምድር ።
፯ አክይስትኒ ፡ ወኵሉ ፡ ቀላያት ።
፰ እሳት፡ወበረድ፡ወአስሐትያ፡ ወሐመዳ፡ መንፈሰ፡ዐውሎ
ዘይገብር ፡ ነቢቦ ።
፱ አድባርኒ ፡ ወኵሉ ፡ አውግር ።
ዕፀውኒ ፡ ዘይፈሪ ፡ ወኵሉ ፡ አርዝ ።
፲ አራዊትኒ ፡ ወኵሉ ፡ እንስሳ ።
ዘይትሐወስኒ ፡ ወአዕዋፍ ፡ ዘይሠርር ።
፲፩ ነገሥተ ፡ ምድርኒ ፡ ወኵሉ ፡ አሕዛብ ።
መላእክትኒ ፡ ወኵሉ ፡ መኳንንተ ፡ ምድር ።
፲፪ ወራዙትኒ ፡ ወደናግል ፡ ሊቃናትኒ ፡ ወመሐዛት ።
፲፫ ይሴብሑ ፡ ለስመ ፡ እግዚአብሔር ።



ልምላሜውንም ፡ ለሰዎች ፡ ግዛት ፡ ያበቅላል ።
ለሚጠሩት ፡ ለቍራዎች ፡ ጫጩቶች ፡ ፱
ለእንስሶችም ፡ ምግባቸውን ፡ ይሰጣል ።
የፈረስን ፡ ኃይል ፡ አፈልግም ፡ ፲
በሰውም ፡ ጭን ፡ አይደሰትም ።
እግዚአብሔር ፡ በሚፈሩት ፡ ፲፩
በምሕረቱም ፡ በሚታመኑ ፡ ይደሰታል ።

መዝሙር ፡ ፻፵፯ ።
ስለ ፡ ትሩፋን ።

ኢየሩሳሌም ፡ ሆይ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኚ ፡ ፩
ጽዮንም ፡ ለአምላክሽ ፡ እልል ፡ በዪ ፡ ፪
የደጆችሽን ፡ መቆለፊያ ፡ አጽንቶአልና ።
ልጆችንም ፡ በውስጥሽ ፡ ባርኳልና ።
በወሰንሽም ፡ ሰላምን ፡ አደረገ ፡ ፫
የስንዴንም ፡ እሸት ፡ አጠገበሽ ።
ነገሩን ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ይሰዳል ፡ ፬
ቃሉም ፡ እጅግ ፡ ፈጥኖ ፡ ይሮጣል ።
አመዳዩን ፡ እንደ ፡ ባዘቶ ፡ ይሰጣል ፡ ፭
ጉሙን፡ እንደ ፡ አመድ ፡ ይበትነዋል ።
በረዶውን ፡ እንደ ፡ ፍርፋሪ ፡ ያወርደዋል ፡ ፮
በበረዶውስ ፡ ፊት ፡ ማን ፡ ይቆማል ?
ቃሉን ፡ ልኮ ፡ ያቀልጠዋል ፡ ፯
ነፋሱን ፡ ያነፍሳል ፡ ውሆችንም ፡ ያፈሳል ።
ቃሉን ፡ ለያዕቆብ ፡ ፰
ሥርዓቱንና ፡ ፍርዱን ፡ ለእስራኤል ፡ ይናገራል ።
ለአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ አላደረገም ፡ ፱
ፍርዱንም ፡ አልገለጠላቸውም ።

መዝሙር ፡ ፻፵፰ ።
ስለ ፡ ትሩፋን ።

ሃሌ ፡ ሉያ ፤ ፩
እግዚአብሔርን ፡ ከሰማያት ፡ አመስግኑት ።
በአርያም ፡ አመስግኑት ።
መላእክቱ ፡ ሁሉ ፡ አመስግኑት ፡ ፪
ሠራዊቱ ፡ ሁሉ ፡ አመስግኑት ።
ፀሐይና ፡ ጨረቃ ፡ አመስግኑት ፡ ፫
ከዋክብትና ፡ ብርሃን ፡ ሁሉ ፡ አመስግኑት ።
ሰማየ ፡ ሰማያት ፡ አመስግኑት ፡ ፬
የሰማያት ፡ በላይም ፡ ውሃ ፡
እርሱ ፡ ብሎአልና ፡ ሆኑም።
እርሱም ፡ አዚልና ፡ ተፈጠሩም ። ፭
የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ ያመስግኑት ።
ለዘላለም ፡ ዓለም ፡ አቆማቸው ፤ ፮
ትእዛዝን ፡ ሰጠ ፡ አያልፉም ።
አባቦች ፡ ጥልቆችም ፡ ሁሉ ፡ ፯
እግዚአብሔርን ፡ ከምድር ፡ አመስግኑት ።
እሳት ፡ በረዶ ፡ አመዳይና ፡ ውርጭ ፡ ፰
ነገሩን ፡ የሚያደርግ ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስም ።
ተራሮች ፡ ኮረብቶችም ፡ ሁሉ ፡ ፱
የሚያፈራም ፡ ዛፍ ፡ ዝግባም ፡ ሁሉ ።
አራዊትም ፡ እንስሳትም ፡ ሁሉ ፡ ፲
ተንቀሳቃሾችም ፡ የሚበሩ ፡ ወፎችም ።
የምድር ፡ ነገሥታት ፡ አሕዛብም ፡ ሁሉ ፡ ፲፩
አለቆች ፡ የምድርም ፡ ፈራጆች ፡ ሁሉ ።
ጐልማሶችና ፡ ቆነጃጅቶች ፡ ፲፪
ሽማግሎችና ፡ ልጆች ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ ያመስግኑ ፡

እስመ ፡ ተለዐለ ፡ ስሙ ፡ ለባሕቲቱ ።
ይገንዩ ፡ ሎቱ ፡ በሰማይ ፡ ወበምድር ።
፲፬ ወያሌዕል ፡ ቀርነ ፡ ሕዝቡ ።
ወስብሐተ ፡ ኵሉ ፡ ጻድቃኑ ።
ለደቂቀ ፡ እስራኤል ፡ ሕዝብ ፡ ዘቅሩብ ፡ ሎቱ ።

መዝሙር ፡ ፻፵፱ ።

በእንተ ፡ ትሩፋን ።

፩ ሃሌ ፡ ሉያ ፤
ሰብሕዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ስብሐተ ፡ ሐዲሰ ።
ስብሐቲሁ ፡ በማኅበረ ፡ ጻድቃን ።
፪ ይትፌሣሕ ፡ እስራኤል ፡ በፈጣሪሁ ።
ወደቂቀ ፡ ጽዮን ፡ ይትሐሠዩ ፡ በንጉሦሙ ።
፫ ወይሴብሑ ፡ ለስሙ ፡ በትፍሥሕት ።
በከበሮ ፡ ወበመዝሙር ፡ ይዜምሩ ፡ ሎቱ ።
፬ እስመ ፡ ሠምረ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሕዝቡ ።
ወያሌዕሎሙ ፡ ለየዋሃን ፡ በአድኅኖቱ ።
፭ ይትሜክሑ ፡ ጻድቃን ፡ በክብሩ ።
ወይትሐሠዩ ፡ በዲበ ፡ ምስካቢሆሙ ።
፮ ወያሌዕልዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በጕርዒቶሙ ።
ሰይፍ ፡ ዘክልኤ ፡ አፉሁ ፡ ውስተ ፡ እደዊሆሙ ።
፯ ከመ ፡ ይግበር ፡ በቀለ ፡ ውስተ ፡ አሕዛብ ።
ወከመ ፡ ይዛለፎሙ ፡ ለሕዝብ ።
፰ ወከመ ፡ ይእስሮሙ ፡ ለነገሥቶሙ ፡ በመዋቅሕት ።
ወለክቡራኒሆሙኒ ፡ በእደ ፡ ሰናስለ ፡ ሐጺን ።
፱ ከመ ፡ ይግበር ፡ ኵነኔ ፡ ዘጽሑፍ ፡ ላዕሌሆሙ ።
ክብር ፡ ይእቲ ፡ ዛቲ ፡ ለኵሉ ፡ ጻድቃኑ ።

መዝሙር ፡ ፻፶ ።

በእንተ ፡ ትሩፋን ።

ሃሌ ፡ ሉያ ፤
፩ ሰብሕዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በቅዱሳኑ ።
ሰብሕዎ ፡ በጽንዐ ፡ ኃይሉ ።
፪ ሰብሕዎ ፡ በክሂሎቱ ።
ሰብሕዎ ፡ በከመ ፡ ብዝኀ ፡ ዕበዩ ።
፫ ሰብሕዎ ፡ በቃለ ፡ ቀርን ።
ሰብሕዎ በመዝሙር ወበመሰንቆ ።
፬ ሰብሕዎ ፡ በከበሮ ፡ ወበትፍሥሕት ።
ሰብሕዎ ፡ በአውታር ፡ ወበዕንዚራ ።
፭ ሰብሕዎ ፡ በጸናጽል ፡ ዘሠናይ ፡ ቃሉ ።
ሰብሕዎ ፡ በጸናጽል ፡ ወበይባቤ ።
፮ ኵሉ ፡ ነፍስ ፡ ይሴብሖ ፡ ለእግዚአብሔር ።

( ውፁእ ፡ እምኍልቍ )

በእንተ ፡ ርእሱ ።

፩ ንዑስ ፡ አነ ፡ እምአኃውየ ።
ወወሬዛ ፡ በቤተ ፡ አቡየ ።
ወእርዒ ፡ አባግዐ ፡ አቡየ ።
፪ እደውየ ፡ ይገብራ ፡ መሰንቆ ።
ወአጻብዕየ ፡ ያስተዋድዳ ፡ መዝሙረ ።
፫ መኑ ፡ ነገሮ ፡ ለእግዚእየ ።
ውእቱ ፡ እግዚአብሔር ፡ ውእቱ ፡ ሰምዐኒ ።
ወውእቱ ፡ ፈነወ ፡ መልአኮ ፡ ወአድኀነኒ ።



ስሙ ፡ ብቻውን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብሎአልና ፤
ምስጋናውም ፡ በሰማይና ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ነው ።
የሕዝቡንም ፡ ቀንድ ፡ ያነሣል ፤ ፲፬
የቅዱሳኑ ፡ ሁሉ ፡ ምስጋና ፤
ወደ ፡ እርሱ ፡ ለቀረበ ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሕዝብ ፡ ነው ።

መዝሙር ፡ ፻፵፱ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

ሃሌ ፡ ሉያ ፤
ለእግዚአብሔር ፡ አዲሱን ፡ ቅኔ ፡ ተቀኙለት ። ፩
ምስጋናው ፡ በቅዱሳኑ ፡ ጉባኤ ፡ ነው ።
እስራኤል ፡ በፈጣሪው ፡ ደስ ፡ ይበለው ፤ ፪
የጽዮንም ፡ ልጆች ፡ በንጉሣቸው ፡ ሐሤትን ፡ ያድርጉ ።
ስሙን ፡ በዘፈን ፡ ያመስግኑ ፤ ፫
በከበሮና ፡ በመሰንቆም ፡ ይዘምሩለት ።
እግዚአብሔር ፡ በሕዝቡ ፡ ተደስቷልና ፤ ፬
የዋሆችንም ፡ በማዳኑ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደርጋልና ።
ቅዱሳን ፡ በክብር ፡ ይመኩ ፤ ፭
በምንጣፋቸውም ፡ ላይ ፡ ሐሤትን ፡ ያደርጋሉ ።
የእግዚአብሔር ፡ ምስጋና ፡ በጉሮሮአቸው ፡ ነው ፤ ፮
ሁለት ፡ አፍ ፡ ያለውም ፡ ሰይፍ ፡ በእጃቸው ፡ ነው ።
በአሕዛብ ፡ ላይ ፡ በቀልን ፤ ፯
በሰዎችም ፡ መካከል ፡ ቅጣትን ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ።
ንጉሦቻቸውን ፡ በሰንሰለት ፤ ፰
አለቆቻቸውንም ፡ በእግር ፡ ብረት ፡ ያስሩ ፡ ዘንድ ።
የተጻፈውን ፡ ፍርድ ፡ ያደርጉባቸው ፡ ዘንድ ፤ ፱
ለቅዱሳን ፡ ሁሉ ፡ ይህች ፡ ክብር ፡ ናት ።

መዝሙር ፡ ፻፶ ።

ስለ ፡ ትሩፋን ።

ሃሌ ፡ ሉያ ፤
እግዚአብሔርን ፡ በመቅደሱ ፡ አመስግኑት ፤ ፩
በኃይሉ ፡ ጠፈር ፡ አመስግኑት ።
በችሎታው ፡ አመስግኑት ፤ ፪
በታላቅነቱ ፡ ብዛት ፡ አመስግኑት ።
በመለከት ፡ ድምፅ ፡ አመስግኑት ፤ ፫
በበገናና ፡ በመሰንቆ ፡ አመስግኑት ።
በከበሮና ፡ በዘፈን ፡ አመስግኑት ፤ ፬
በአውታርና ፡ በእምቢልታ ፡ አመስግኑት ።
ድምፁ ፡ መልካም ፡ በሆነ ፡ ጸናጽል ፡ አመስግኑት ፤ ፭
እልልታ ፡ በአለው ፡ ጸናጽል ፡ አመስግኑት ።
እስትንፋስ ያለው ሁሉ እግዚአብሔርን ያመስግን ። ፮
ሃሌ ፡ ሉያ ።

ስለ ፡ ራሱ ፡ ( ከቍጥር ፡ ያልገባ ። )

ከወንድሞቼ ፡ ይልቅ ፡ ትንሽ ፡ ነበርኩ ፤ ፩
በአባቴ ፡ ቤትም ፡ ወጣት ፡ ነበርኩ ፤
ያባቴን ፡ በጎችም ፡ እጠብቅ ፡ ነበር ።
እጆቼ ፡ መሰንቆ ፡ ይመቱ ፡ ነበር ፤ ፪
ጣቶቼም ፡ በገና ፡ ይደረድሩ ፡ ነበር ።
ለጌታዬ ፡ ማን ፡ ነገረው ? ፫
እርሱ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሰማኝ ፡ እንጂ ።
እርሱም ፡ መልአኩን ፡ ልኮ ፡ አዳነኝ ።

፭ ወነሥአኒ ፡ እምአባግዐ ፡ አቡየ ።
ወቀብዐኒ ፡ ቅብዐ ፡ ቅዱሰ ።
፮ አኃውየሰ ፡ ሠናያን ፡ ወልሂቃን ።
ወኢሠምረ ፡ ቦሙ ፡ እግዚአብሔር ።
፯ ወወፃእኩ ፡ ለተእኅዞቱ ፡ ለሕዝብ ፡ ነኪር ።
ወረገመኒ ፡ በአማልክቲሆሙ ፡ ርኩሳን ።
፰ ወአንስ ፡ ነሣእኩ ፡ እዕባነ ፡ እምውስተ ፡ ፈለግ ።
ወወጸፍክዎ ፡ ውስተ ፡ ፍጽሙ ።
አሜሃ ፡ ወድቀ ፡ በኃይለ ፡ እግዚአብሔር ።
፱ ወአንስ ፡ ነሣእኩ ፡ ዘእምላዕሌሁ ፡ ሰይፈ ።
ወመተርኩ ፡ ርእሶ ፡ ሰጎልያድ ።
ወአሰሰልኩ ፡ ጽዕለተ ፡ እምደቂቀ ፡ እስራኤል ።





የአባቴን ፡ በጎች ፡ ከምጠብቅበት ፡ መረጠኝ ፤ ፭
ክቡር ፡ ቅብዐ ፡ መንግሥትን ፡ ቀብቶ ፡ አነገሠኝ ፤
ወንድሞቼ ፡ ግን ፡ በመልክ ፡ ያማሩ ፡ በዕድሜ ፡ ያደጉ ፮
ናቸው ፤
እግዚአብሔር ፡ አላደረባቸውም ።
ልዩ ፡ ወገንን ፡ ሊያያዘው ፡ ሊገጥመውም ፡ ወጣሁ ፤ ፯
በረከሱ ፡ ጣዖቶቹም ፡ ረገመኝ ።
እኔም ፡ ከወንዝ ፡ ደንጊያዎችን ፡ አነሣሁና ፡ አወንጭፌ ፡ ፰
ግንባሩን ፡ መታሁት ።
ያን፡ጊዜም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ኃይል ፡ ወደቀ ።
የታጠቀውንም፡ ሰይፍ ፡ ነጥቄ ፡ ያዝሁ ፡ የጎልያድንም ፱
ራሱን ፡ ቆረጥሁ ።
ከእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ስድብን ፡ አራቅሁ ።



# መጽሐፈ፡ምሳሌ።

(ክለሳ.1.20020507)

## መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡1።

ምዕራፍ፡1፤

1፤የእስራኤል፡ንጉሥ፡የዳዊት፡ልጅ፡የሰሎሞን፡ምሳሌዎች፤

2፤ጥበብንና፡ተግሣጽን፡ለማወቅ፥የዕውቀትንም፡ቃል፡ለማስተዋል፥

3፤የጥበብን፡ትምህርት፡ጽድቅንና፡ፍርድን፡ቅንነትንም፡ለመቀበል፥

4፤ብልኅትን፡ለአላዋቂዎች፡ይሰጥ፡ዘንድ፥ለጐበዛዝትም፡ዕውቀትንና፡ጥንቃቄን፥

5፤ጠቢብ፡እነዚህን፡ከመስማት፡ጥበብን፡ይጨምራል፥አስተዋይም፡መልካም፡ምክርን፡ገንዘቡ፡ያደርጋል።

6፤ምሳሌንና፡ትርጓሜን፥የጠቢባንን፡ቃልና፡የተሸሸገውን፡ነገር፡ለማስተዋል።

7፤የጥበብ፡መዠመሪያ፡እግዚአብሔርን፡መፍራት፡ነው፤ሰነፎች፡ግን፡ጥበብንና፡ተግሣጽን፡ይንቃሉ።

8፤ልጄ፡ሆይ፥የአባትኽን፡ምክር፡ስማ፥የእናትኽንም፡ሕግ፡አትተው፤

9፤ለራስኽ፡የሞገስ፡ዘውድ፡ለዐንገትኽም፡ድሪ፡ይኾንልኻልና።

10፤ልጄ፡ሆይ፥ኀጢአተኛዎች፡ቢያባብሉኽ፡ዕሺ፡አትበል።

11፤ደምን፡ለማፍሰስ፡ከእኛ፡ጋራ፡ና፡እናድባ፥ለንጹሕም፡ያለምክንያት፡ወጥመድን፡እንሸምቅበት፡ቢሉ፤

12፤በሕይወታቸው፡ሳሉ፡እንደ፡ሲኦል፡ኾነን፡እንዋጣቸው፥በሙሉም፡ወደ፡ጕድጓድ፡እንደሚወድቁ፡ይኹኑ፤

13፤መልካሙን፡ሀብት፡ዅሉ፡እናገኛለን፥ከምርኮውም፡ቤታችንን፡እንሞላለን፤

14፤ዕጣኽን፡ከእኛ፡ጋራ፡ጣል፤ለዅላችንም፡አንድ፡ከረጢት፡ይኹን፡ቢሉ፤

15፤ልጄ፡ሆይ፥ከነርሱ፡ጋራ፡በመንገድ፡አትኺድ፥ከጐዳናቸውም፡እግርኽን፡ፈቀቅ፡አድርግ፤

16፤እግሮቻቸው፡ወደ፡ክፋት፡ይሮጣሉና፥ደም፡ለማፍሰስም፡ይፈጥናሉና።

17፤መርበብ፡በወፎች፡ዐይን፡ፊት፡በከንቱ፡ትተከላለችና።

18፤እነርሱም፡በደማቸው፡ላይ፡ያደባሉ፥በነፍሳቸውም፡ላይ፡ይሸምቃሉ።

19፤እንዲሁ፡ይህ፡መንገድ፡ትርፍን፡ለማግኘት፡የሚሣሣ፡ዅሉ፡ነው።የባለቤቱን፡ነፍስ፡ይነጥቃል።

20፤ጥበብ፡በጐዳና፡ትጮኻለች፤በአደባባይ፡ድምፃን፡ከፍ፡ታደርጋለች፤

21፤በአደባባይ፡ትጣራለች፤በከተማዪቱ፡መግቢያ፡በር፡ቃልን፡ትናገራለች።

22፤እናንተ፡አላዋቂዎች፥እስከ፡መቼ፡አላዋቂነት፡ትወዷላችኹ፤ፌዘኛዎችም፡ፌዝን፡ይፈቅዳሉ፤ሰነፎችም፡ዕው ቀትን፡ይጠላሉ፤

23፤ወደ፡ዘለፋዬ፡ተመለሱ፤እንሆ፥መንፈሴን፡አፈሽላችኋለኹ፤ቃሌን፡አስተምራችኋለኹ።

24፤በጠራዅ፡ጊዜ፡እምቢ፡ስላላችኹ፥እጄን፡በዘረጋኹ፡ጊዜ፡ማንም፡ስላላስተዋለ፥

25፤ምክሬን፡ዅሉ፡ግን፡ቸል፡ስላላችኹ፥ዘለፋዬንም፡ስላልፈቀዳችኹ፤

26፤እኔም፡ስለዚህ፡በጥፋታችኹ፡እሥቃለኹ፤ጥፋታችኹም፡በመጣ፡ጊዜ፡አላግጥባችኋለኹ።

27፤ድንጋጤ፡እንደ፡ጐርፍ፡በደረሰባችኹ፡ጊዜ፥ጥፋታችኹም፡እንደ፡ዐውሎ፡ነፋስ፡በመጣ፡ጊዜ፥ጭንቅና፡መከራ፡ በወረደባችኹ፡
ጊዜ።

28፤የዚያን፡ጊዜ፡ይጠሩኛል፥እኔ፡ግን፡አልመልስም፤ተግተው፡ይሹኛል፥ነገር፡ግን፥አያገኙኝም።

29፤ዕውቀትን፡ጠልተዋልና፥እግዚአብሔርንም፡መፍራት፡አልመረጡምና፤

30፤ምክሬን፡አልፈቀዱምና፥ዘለፋዬንም፡ዅሉ፡ንቀዋልና፤

31፤ስለዚህ፥የመንገዳቸውን፡ፍሬ፡ይበላሉ፥ከራሳቸው፡ምክር፡ይጠግባሉ።

32፤አላዋቂዎችን፡ከጥበብ፡መራቅ፡ይገድላቸዋልና፥ሰነፎችንም፡ቸልተኛ፡መኾን፡ያጠፋቸዋልና።

33፤የሚሰማኝ፡ግን፡በርጋታ፡ይቀመጣል፥ከመከራም፡ሥጋት፡ያርፋል።

__________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡2።_________________

ምዕራፍ፡2፤

1፤ልጄ፡ሆይ፥ቃሌን፡ብትቀበል፥ትእዛዜንም፡ባንተ፡ዘንድ፡ሸሽገኽ፡ብትይዛት፥

2፤ጆሮኽ፡ጥበብን፡እንዲያደምጥ፡ታደርጋለኽ፥ልብኽንም፡ወደ፡ማስተዋል፡ታዘነብላለኽ።

3፤ረቂቅ፡ዕውቀትን፡ብትጠራት፥ለማስተዋልም፡ድምፅኽን፡ብታነሣ፥

4፤ርሷንም፡እንደ፡ብር፡ብትፈላልጋት፥ርሷንም፡እንደ፡ተቀበረ፡ገንዘብ፡ብትሻት፤

5፤የዚያን፡ጊዜ፡እግዚአብሔርን፡መፍራት፡ታውቃለኽ፥የአምላክንም፡ዕውቀት፡ታገኛለኽ።

6፤እግዚአብሔር፡ጥበብን፡ይሰጣልና፤ከአፉም፡ዕውቀትና፡ማስተዋል፡ይወጣሉ፤

7፤ርሱ፡ለቅኖች፡ደኅንነትን፡ያከማቻል፤ያለነውር፡ለሚኼዱትም፡ጋሻ፡ነው፤

8፤የፍርድን፡ጐዳና፡ይጠብቃል፤የቅዱሳኑንም፡መንገድ፡ያጸናል።

9፤የዚያን፡ጊዜ፡ጽድቅንና፡ፍርድን፡ቅንነትንና፡መልካም፡መንገድን፡ኹሉ፡ታስተውላለኽ።

10፤ጥበብ፡ወደ፡ልብኽ፡ትገባለችና፥ዕውቀትም፡ነፍስኽን፡ደስ፡ታሠኛለችና፤

11፤ጥንቃቄ፡ይጠብቅኻል፥ማስተዋልም፡ይጋርድኻል፥

12፤ከክፉ፡መንገድ፡አንተን፡ለማዳን፥ጠማማ፡ነገርን፡ከሚናገሩም፡ሰዎች፤

13፤እነርሱም፡በጨለማ፡መንገድ፡ይኼዱ፡ዘንድ፡የቀናውን፡ጐዳና፡የሚተዉ፥

14፤ክፉ፡በመሥራት፡ደስ፡የሚላቸው፡በጠማማነትም፡ደስታን፡የሚያደርጉ፥

15፤መንገዳቸውን፡የሚጠመዝዙ፥አካኼዳቸውንም፡የሚያጣምሙ፡ናቸው፤

16፤ከጋለሞታ፡ሴት፡አንተን፡ለመታደግ፥ቃሏን፡ከምታለዝብ፡ከሌላዪቱም፡ሴት፤

17፤የሕፃንነት፡ወዳጇን፡የምትተው፡የአምላኳንም፡ቃል፡ኪዳን፡የምትረሳ፤

18፤ቤቷ፡ወደ፡ሞት፡ያዘነበለ፡ነው፥አካኼዷም፡ወደሙታን፡ጥላ።

19፤ወደ፡ርሷ፡የሚገቡ፡ኹሉ፡አይመለሱም፥የሕይወትንም፡ጐዳና፡አያገኙም፤

20፤አንተም፡በደጋግ፡ሰዎች፡መንገድ፡እንድትኼድ፡የጻድቃንንም፡ጐዳና፡እንድትጠብቅ።

21፤ቅኖች፡በምድር፡ላይ፡ይቀመጣሉና፥ፍጹማንም፡በርሷ፡ይኖራሉና፤

22፤ኃጥኣን፡ግን፡ከምድር፡ይጠፋሉ፥ዐመፀኞችም፡ከርሷ፡ይነጠቃሉ።

__________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡3።_________________

ምዕራፍ፡3፤

1፤ልጄ፡ሆይ፥ሕጌን፡አትርሳ፥ልብኽም፡ትእዛዟን፡ይጠብቅ።

2፤ብዙ፡ዘመናትና፡ረዥም፡ዕድሜ፡ሰላምም፡ይጨምሩልኻልና።

3፤ምሕረትና፡እውነት፡ከአንተ፡አይራቁ፤በዐንገትኽ፡እሰራቸው፤በልብኽ፡ጽላት፡ጻፋቸው።

4፤በእግዚአብሔርና፡በሰው፡ፊትም፡ሞገስንና፡መልካም፡ዝናን፡ታገኛለኽ።

5፤በፍጹም፡ልብኽ፡በእግዚአብሔር፡ታመን፥በራስኽም፡ማስተዋል፡አትደገፍ፤

6፤በመንገድኽ፡ኹሉ፡ርሱን፡ዕወቅ፥ርሱም፡ጐዳናኽን፡ያቀናልኻል።

7፤በራስኽ፡አስተያየት፡ጠቢብ፡አትኹን፤እግዚአብሔርን፡ፍራ፥ከክፋትም፡ራቅ፤

8፤ይህም፡ለሥጋኽ፡ፈውስ፡ይኾንልኻል፥ለዐጥንትኽም፡ጠገን።

9፤እግዚአብሔርን፡ከሀብትኽ፡አክብር፥ከፍሬኽም፡ኹሉ፡በኵራት፤

10፤ጐተራኽም፡እኽልን፡ይሞላል፥መጥመቂያኽም፡በወይን፡ጠጅ፡ሞልታ፡ትትረፈረፋለች።

11፤ልጄ፡ሆይ፥የእግዚአብሔርን፡ተግሣጽ፡አትናቅ፥በገሠጸኽም፡ጊዜ፡አትመረር።

12፤እግዚአብሔር፡የወደደውን፡ይገሥጸልና፥አባት፡የሚወደውን፡ልጁን፡እንደሚገሥጽ።

13፤ጥበብን፡የሚያገኝ፡ሰው፡ምስጉን፡ነው፥ማስተዋልንም፡ገንዘቡ፡የሚያደርግ፤

14፤በወርቅና፡በብር፡ከመነገድ፡ይልቅ፡በርሷ፡መነገድ፡ይሻላልና።
15፤ከቀይ፡ዕንቍም፡ትከብራለች፥የተከበረም፡ነገር፡ዅሉ፡አይተካከላትም።
16፤በቀኟ፡ረዥም፡ዘመን፡ነው፥በግራዋም፡ባለጠግነትና፡ክብር።
17፤መንገዷ፡የደስታ፡መንገድ፡ነው፥ጐዳናዋም፡ዅሉ፡ሰላም፡ነው።
18፤ርሷ፡ለሚይዟት፡የሕይወት፡ዛፍ፡ናት፥የተመረኰዘባትም፡ዅሉ፡ምስጉን፡ነው።
19፤እግዚአብሔር፡በጥበብ፡ምድርን፡መሠረተ፥በማስተዋልም፡ሰማያትን፡አጸና።
20፤በዕውቀቱ፡ቀላያት፡ተቀደዱ፥ደመናትም፡ጠልን፡ያንጠባጥባሉ።
21፤ልጄ፡ሆይ፥እነዚህ፡ከዐይኖችኽ፡አይራቁ፤መልካም፡ጥበብንና፡ጥንቃቄን፡ጠብቅ።
22፤ለነፍስኽም፡ሕይወት፡ይኾናሉ፥ለዐንገትኽም፡ሞገስ።
23፤የዚያን፡ጊዜ፡መንገድኽን፡ተማምነኽ፡ትኼዳለኽ፥እግርኽም፡አይሰነካከልም።
24፤በተኛኽ፡ጊዜ፡አትፈራም፤ትተኛለኽ፥እንቅልፍኽም፡የጣፈጠ፡ይኾንልኻል።
25፤ድንገት፡ከሚያስፈራ፡ነገር፥ከሚመጣውም፡ከኃጥኣን፡ጥፋት፡አትፈራም፤
26፤እግዚአብሔር፡መታመኛኽ፡ይኾናልና፥እግርኽም፡እንዳይጠመድ፡ይጠብቅኻልና።
27፤ለተቸገረው፡ሰው፡በጎ፡ነገርን፡ማድረግ፡አትከልክል፥ልታደርግለት፡የሚቻልኽ፡ሲኾን።
28፤ወዳጅኽን፡-ኺድና፡ተመለስ፤ነገ፡እሰጥኻለኹ፡አትበለው፥በጎ፡ነገርን፡ማድረግ፡ሲቻልኽ።
29፤በወዳጅኽ፡ላይ፡ክፉ፡አትሥራ፥ርሱ፡ተማምኖ፡ከአንተ፡ጋራ፡ተቀምጦ፡ሳለ።
30፤ከሰው፡ጋራ፡በከንቱ፡አትጣላ፥ርሱ፡ክፉ፡ካልሠራብኽ።
31፤በግፈኛ፡ሰው፡አትቅና፥መንገዱንም፡ዅሉ፡አትምረጥ።
32፤ጠማማ፡ዅሉ፡በእግዚአብሔር፡ፊት፡ርኩስ፡ነውና፤ወዳጅነቱ፡ግን፡ከቅኖች፡ጋራ፡ነው።
33፤የእግዚአብሔር፡መርገም፡በኃጥእ፡ቤት፡ነው፥የጻድቃን፡ቤት፡ግን፡ይባረካል።
34፤በፌዘኞዎች፡ርሱ፡ያፌዛል፥ለትሑታን፡ግን፡ሞገስን፡ይሰጣል።
35፤ጠቢባን፡ክብርን፡ይወርሳሉ፤የሰነፎች፡ከፍታቸው፡ግን፡መዋረድ፡ነው።
__________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡4።__________________

ምዕራፍ፡4፤
1፤እናንተ፡ልጆች፥የአባትን፡ተግሣጽ፡ስሙ፥ማስተዋልንም፡ታውቁ፡ዘንድ፡አድምጡ፤
2፤መልካም፡ትምህርትን፡እሰጣችኋለኹና፤ሕጌን፡አትተዉ።
3፤እኔም፡አባቴን፡የምሰማ፡ልጅ፡ነበርኹና፥በእናቴም፡ዘንድ፡እወደድ፡ነበር።
4፤ያስተምረኝም፡ነበር፡እንዲህም፡ይለኝ፡ነበር፡-ልብኽ፡ቃሌን፡ይቀበል፤ትእዛዜን፡ጠብቅ፡በሕይወትም፡ትኖራለ ኽ።
5፤ጥበብን፡አግኝ፤ማስተዋልን፡አግኝ፤አትርሳም፥ከአፌም፡ቃል፡ፈቀቅ፡አትበል።
6፤አትተዋት፥ትደግፍኽማለች፤ውደዳት፥ትጠብቅኽማለች።
7፤ጥበብ፡ዐይነተኛ፡ነገር፡ናትና፥ጥበብን፡አግኝ፤ከሀብትኽም፡ዅሉ፡ማስተዋልን፡አትርፍ።
8፤ከፍ፡ከፍ፡አድርጋት፥ርሷም፡ከፍ፡ከፍ፡ታደርግኻለች፤ብታቅፋትም፡ታከብርኻለች።
9፤ለራስኽ፡የሞገስ፡አክሊልን፡ትሰጥኻለች፥የተዋበ፡ዘውድንም፡ታበረክትኻለች።
10፤ልጄ፡ሆይ፥ስማ፥ንግግሬንም፡ተቀበል፤የሕይወትኽም፡ዘመን፡ትበዛልኻለች።
11፤የጥበብን፡መንገድ፡አስተማርኹኽ፤በቀናች፡ጐዳና፡መራኹኽ።
12፤በኼድኽ፡ጊዜ፡ርምጃኽ፡አይጠብብም፤በሮጥኽም፡ጊዜ፡አትሰናከልም።
13፤ተግሣጽን፡ያዝ፥አትተውም፤ጠብቀው፥ርሱ፡ሕይወትኽ፡ነውና።
14፤በኃጥኣን፡መንገድ፡አትግባ፥በክፉ፡ሰዎችም፡ጐዳና፡አትኺድ።
15፤ከርሷ፡ራቅ፥አትኺድባትም፤ፈቀቅ፡በል፥ተዋትም።
16፤ክፉ፡ካላደረጉ፡አይተኙምና፥ካላሰናከሉም፡እንቅልፋቸው፡ይወገዳልና።

17፤የኀጢአትን፡እንጀራ፡ይበላሉና፥የግፍንም፡ወይን፡ጠጅ፡ይጠጣሉና።
18፤የጻድቃን፡መንገድ፡ግን፡እንደ፡ንጋት፡ብርሃን፡ነው፥ሙሉ፡ቀን፡እስኪኾንም፡ድረስ፡እየተጨመረ፡ይበራል።
19፤የኃጥኣን፡መንገድ፡እንደ፡ጨለማ፡ነው፥እንዴት፡እንደሚሰናከሉም፡አያውቁም።
20፤ልጄ፡ሆይ፥ንግግሬን፡አድምጥ፡ወደ፡ቃሌም፡ዦሮኽን፡አዘንብል።
21፤ከዐይንኽ፡አታርቃት፥በልብኽም፡ውስጥ፡ጠብቃት።
22፤ለሚያገኟት፡ሕይወት፥ለሥጋቸውም፡ዅሉ፡ፈውስ፡ነውና።
23፤አጥብቀኽ፡ልብኽን፡ጠብቅ፥የሕይወት፡መውጫ፡ከርሱ፡ነውና።
24፤የአፍኽን፡ጠማማነት፡ከአንተ፡አውጣ፥ሐሰተኛዎቹን፡ከንፈሮችም፡ከአንተ፡አርቅ።
25፤ዐይኖችኽ፡አቅንተው፡ይዩ፥ሽፋሽፍቶችኽም፡በቀጥታ፡ይመልከቱ።
26፤የእግርኽን፡መንገድ፡አቅና፥አካኼድኽም፡ዅሉ፡ይጽና።
27፤ወደ፡ቀኝም፡ወደ፡ግራም፡አትበል፤እግርኽንም፡ከክፉ፡መልስ።
__________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡5።_________________
ምዕራፍ፡5፤
1፤ልጄ፡ሆይ፥ወደ፡ጥበቤ፡አድምጥ፤ዦሮኽን፡ወደ፡ትምህርቴ፡መልስ፥
2፤ጥንቃቄን፡ትጠብቅ፡ዘንድ፡ከንፈሮችኽም፡ዕውቀትን፡እንዲጠብቁ።
3፤ከጋለሞታ፡ሴት፡ከንፈር፡ማር፡ይንጠባጠባልና፥አፏም፡ከቅቤ፡የለሰለሰ፡ነውና፤
4፤ፍጻሜዋ፡ግን፡እንደ፡ሬት፡የመረረ፡ነው፥ኹለት፡አፍ፡እንዳለው፡ሰይፍም፡የተሳለ፡ነው።
5፤እግሮቿ፡ወደ፡ሞት፡ይወርዳሉ፥አረማመዷም፡ወደ፡ሲኦል፡ነው፤
6፤የቀና፡የሕይወትን፡መንገድ፡አታገኝም፤በአካኼዷ፡የተቅበዘበዘች፡ናት፥የሚታወቅም፡አይደለም።
7፤አኹንም፡ልጆቼ፡ሆይ፥ስሙኝ፥ከአፌም፡ቃል፡አትራቁ።
8፤መንገድኽን፡ከርሷ፡አርቅ፥ወደቤቷም፡ደጅ፡አትቅረብ፥
9፤ክብርኽ፡ለሌላ፡እንዳትሰጥ፥ዕድሜኽም፡ለጨካኝ፤
10፤ሌላዎች፡ከሀብትኽ፡እንዳይጠግቡ፥ድካምኽም፡በባዕድ፡ሰው፡ቤት፡እንዳይኾን።
11፤በመጨረሻም፡ሥጋኽና፡ሰውነትኽ፡በጠፉ፡ጊዜ፡ታለቅሳለኽ፥
12፤ትላለኽም፦እንዴት፡ትምህርትን፡ጠላኹ፥ልቤም፡ዘለፋን፡ናቀ!
13፤የአስተማሪዎቼንም፡ቃል፡አልሰማኹም፥ዦሮዎቼንም፡ወደ፡አስተማሪዎቼ፡አላዘነበልኹም።
14፤በማኅበርና፡በጉባኤ፡መካከል፡ወደ፡ክፉ፡ዅሉ፡ለመድረስ፡ጥቂት፡ቀረኝ።
15፤ከጒድጓድኽ፡ውሃ፥ከምንጭኽም፡የሚፈልቀውን፡ውሃ፡ጠጣ።
16፤ምንጮችኽ፡ወደ፡ሜዳ፥ወንዞችኽ፡ወደ፡አደባባይ፥ይፈሷሉን፤
17፤ለአንተ፡ብቻ፡ይኹኑ፥ከአንተ፡ጋራ፡ላሉ፡እንግዳዎችም፡አይኹኑ።
18፤ምንጭኽ፡ቡሩክ፡ይኹን፤ከጒብዝናኽም፡ሚስት፡ጋራ፡ደስ፡ይበልኽ።
19፤እንደ፡ተወደደች፡ዋላ፡እንደ፡ተዋበችም፡ሚዳቋ፥ጡቷ፡ዅልጊዜ፡ታርካኽ፥በፍቅሯም፡ዅልጊዜ፡ጥገብ።
20፤ልጄ፡ሆይ፥ስለ፡ምን፡ጋለሞታ፡ሴት፡ትወዳለኽ፤የሌላዪቱንስ፡ብብት፡ለምን፡ታቅፋለኽ፤
21፤የሰው፡መንገድ፡በእግዚአብሔር፡ፊት፡ነውና፥አካኼዱንም፡ዅሉ፡ርሱ፡ይመለከታልና።
22፤ኃጥኣንን፡ኀጢአቱ፡ታጠምደዋለች፥በኀጢአቱም፡ገመድ፡ይታሰራል።
23፤አልተቀጣምና፡ርሱ፡ይሞታል፤በስንፍናውም፡ብዛት፡ይስታል።
__________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡6።_________________
ምዕራፍ፡6፤
1፤ልጄ፡ሆይ፥ለጎረቤትኽ፡ዋስ፡ብትኾን፥ስለ፡ሌላ፡ሰው፡እጅኽን፡ኢጋና፡ብትመታ፥
2፤በአፍኽ፡ቃል፡ተጠመድኽ፤በአፍኽ፡ቃል፡ተያዝኽ።

3፤ልጄ፡ሆይ፥ይህን፡አድርግ፡ራስኽንም፡አድን፥በጎረቤትኽ፡እጅ፡ወድቀኻልና፤ፈጥነኽ፡ኺድ፥ጎረቤትኽንም፡ነዝ ንዘው።
4፤ለዐይንኽ፡እንቅልፍን፡ለሽፋሽፍቶችኽም፡እንጕልቻን፡አትስጥ፥
5፤እንደ፡ሚዳቋ፡ከአዳኝ፡እጅ፥እንደ፡ወፍም፡ከአጥማጅ፡እጅ፡ትድን፡ዘንድ።
6፤አንተ፡ታካች፥ወደ፡ገብረ፡ጕንዳን፡ኺድ፥መንገዷንም፡ተመልክተኽ፡ጠቢብ፡ኹን።
7፤አለቃና፡አዛዥ፡ገዢም፡ሳይኖራት፡
8፤መብሏን፡በበጋ፡ታሰናዳለች፥መኖዋንም፡በመከር፡ትሰበስባለች።
9፤አንተ፡ታካች፥እስከ፡መቼ፡ትተኛለኽ፤ከእንቅልፍኽስ፡መቼ፡ትነሣለኽ፤
10፤ጥቂት፡ትተኛለኽ፥ጥቂት፡ታንቀላፋለኽ፥ትተኛም፡ዘንድ፡ጥቂት፡እጅኽን፡ታጥፋለኽ፤
11፤እንግዲህ፡ድኽነትኽ፡እንደ፡ወንበዴ፥ችጋርኽም፡ሰይፍ፡እንደ፡ታጠቀ፡ሰው፡ይመጣብኻል።
12፤ምናምንቴ፡ሰው፡የበደለኛም፡ልጅ፡በጠማማ፡አፍ፡ይኼዳል፤
13፤በዐይኑ፡ይጠቅሳል፥በእግሩ፡ይናገራል፥በጣቱ፡ያስተምራል፤
14፤ጠማማነት፡በልቡ፡አለ፥ኹልጊዜም፡ክፉትን፡ያስባል፤ጠብንም፡ይዘራል።
15፤ስለዚህ፥ጥፋቱ፡ድንገት፡ይደርስበታል፤ድንገት፡ይደቃል፥ፈውስም፡ከቶ፡የለውም።
16፤እግዚአብሔር፡የሚጠላቸው፡ስድስት፡ነገሮች፡ናቸው፥ሰባትንም፡ነፍሱ፡አጥብቃ፡ትጸየፈዋለች፤
17፤ትዕቢተኛ፡ዐይን፥ሐሰተኛ፡ምላስ፥ንጹሕን፡ደም፡የምታፈስ፡እጅ፥
18፤ክፉ፡ዐሳብን፡የሚያበቅል፡ልብ፥ወደ፡ክፉ፡የምትሮጥ፡እግር፥
19፤በሐሰት፡የሚናገር፡ሐሰተኛ፡ምስክር፡በወንድማማች፡መካከልም፡ጠብን፡የሚዘራ።
20፤ልጄ፡ሆይ፥የአባትኽን፡ትእዛዝ፡ጠብቅ፥የእናትኽንም፡ሕግ፡አትተው፤
21፤ኹልጊዜም፡በልብኽ፡አኑረው፥በዐንገትኽም፡እሰረው።
22፤ስትኼድም፡ይመራኻል፤ስትተኛ፡ይጠብቅኻል፤ስትነሣ፡ያነጋግርኻል።
23፤ትእዛዝ፡መብራት፥ሕግም፡ብርሃን፡ነውና፥የተግሣጽም፡ዘለፋ፡የሕይወት፡መንገድ፡ነውና፥
24፤ከክፉ፡ሴት፡ትጠብቅኽ፡ዘንድ፥ከሌላዪቱም፡ሴት፡ምላስ፡ጥፍጥነት።
25፤ውበቷን፡በልብኽ፡አትመኘው፤ሽፋሽፍቷም፡አያጥምድኽ።
26፤የጋለሞታ፡ዋጋ፡እስከ፡አንዲት፡እንጀራ፡ነው፤አመንዝራም፡ሴት፡የሰውን፡ሕይወት፡ታጠምዳለች።
27፤በጕያው፡እሳትን፡የሚታቀፍ፥ልብሶቹስ፡የማይቃጠሉ፡ማን፡ነው፤
28፤በፍም፡ላይ፡የሚኼድ፡እግሮቹስ፡የማይቃጠሉ፡ማን፡ነው፤
29፤ወደሰው፡ሚስት፡የሚገባም፡እንዲሁ፡ነው፤የሚነካትም፡ኹሉ፡ሳይቀጣ፡አይቀርም።
30፤ሌባ፡በተራበ፡ጊዜ፡ነፍሱን፡ሊያጠግብ፡ቢሰርቅ፡ሰዎች፡አይንቁትም፤
31፤ቢያዝም፡ሰባት፡ዕጥፍ፡ይከፍላል፥በቤቱም፡ያለውን፡ኹሉ፡ይሰጣል።
32፤ከሴት፡ጋራ፡የሚያመነዝር፡ግን፡አእምሮው፡የጐደለ፡ነው፤እንዲሁም፡የሚያደርግ፡ነፍሱን፡ያጠፋል።
33፤ቍስልንና፡ውርደትን፡ያገኛል፥ስድቡም፡አይደመሰስም።
34፤ቅንአት፡ለሰው፡የቍጣ፡ትኵሳት፡ነውና፥በበቀል፡ቀን፡አይራራለትምና።
35፤ርሱም፡ምንም፡ካሳ፡አይቀበልም፥ስጦታም፡ብታበዛለት፡አይታረቅም።
___________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡7።__________________
ምዕራፍ፡7፤
1፤ልጄ፡ሆይ፥ቃሌን፡ጠብቅ፡ትእዛዜንም፡ባንተ፡ዘንድ፡ሸሽግ።
2፤ትእዛዜን፡ጠብቅ፡በሕይወትም፡ትኖራለኽ፤ሕጌንም፡እንደ፡ዐይንኽ፡ብሌን፡ጠብቅ፤
3፤በጣቶችኽ፡እሰራቸው፤በልብኽ፡ጽላት፡ጻፋቸው።
4፤ጥበብን፦አንቺ፡እኅቴ፡ነሽ፡በላት፥ማስተዋልንም፦ወዳጄ፡ብለኽ፡ጥራት፥
5፤ከጋለሞታ፡ሴት፡ትጠብቅኽ፡ዘንድ፡ቃሏን፡ካለዘበች፡ከሌላዪቱ፡ሴት።

6፤በቤቴ፡መስኮት፡ኾኜ፡ወደ፡አደባባይ፡ተመለከትኹ፤

7፤ካላዋቂዎች፡መካከል፡አስተዋልኹ፤ከጐበዛዝትም፡መካከል፡ብላቴናውን፡አእምሮ፡ጐድሎት፡አየኹ፥

8፤በአደባባይ፡ሲኼድ፡በቤቷም፡አቅራቢያ፡ሲያልፍ፤የቤቷን፡መንገድ፡ይዞ፡ወደ፡ርሷ፡አቀና፥

9፤ማታ፡ሲመሽ፥ውድቅትም፡ሲኾን፥በሌሊትም፡በጽኑ፡ጨለማ።

10፤እንሆ፥ሴት፡ተገናኘችው፥የጋለሞታ፡ልብስ፡የለበሰች፥ነፍሳትን፡ለማጥመድ፡የተዘጋጀች።

11፤ሁከተኛና፡አባያ፡ናት፥እግሮቿም፡በቤቷ፡አይቀመጡም፤

12፤አንድ፡ጊዜ፡በጐዳና፥አንድ፡ጊዜ፡በአደባባይ፥በማእዘኑም፡ዅሉ፡ታደባለች።

13፤ያዘችውም፥ሳመችውም፤ፊቷም፡ያለዕፍረት፡ኾኖ፡እንዲህ፡አለችው፦

14፤መሥዋዕትንና፡የደኅንነት፡ቍርባንን፡ማቅረብ፡ነበረብኝ፤ዛሬ፡ስእለቴን፡ፈጸምኹ።

15፤ስለዚህ፥እንድገናኝኽ፥ፊትኽንም፡በትጋት፡ለመሻት፡ወጥቻለኹ፥አግኝቼኻለኹም።

16፤በዐልጋዬ፡ላይ፡ማለፊያ፡ሰርፍ፡ዘርግቼበታለኹ፥የግብጽንም፡ሽመልመሌ፡ለሐፍ።

17፤በመኝታዬ፡ከርቤንና፡ዓልሙን፣ቀረፋም፡ረጭቼበታለኹ።

18፤ና፥እስኪነጋ፡ድረስ፡በፍቅር፡እንርካ፥በተወደደ፡መተቃቀፍም፡ደስ፡ይበለን።

19፤ባለቤቴ፡በቤቱ፡የለምና፥ወደ፡ሩቅ፡መንገድ፡ኼዷልና፤

20፤በእጁም፡የብር፡ከረጢት፡ወስዷል፤ሙሉ፡ጨረቃ፡በኾነች፡ጊዜ፡ወደ፡ቤቱ፡ይመለሳል።

21፤በብዙ፡ጨዋታዋ፡እንዲስት፡ታደርገዋለች፤በከንፈሯ፡ልዝብነት፡ትጐትተዋለች።

22፤ርሱ፡እንዲህ፡ስቶ፡ይከተላታል፥በሬ፡ለመታረድ፡እንዲነዳ፥ውሻም፡ወደ፡እስራት፡እንዲኼድ፥

23፤ወፍ፡ወደ፡ወጥመድ፡እንደሚቸኵል፥ለነፍሱ፡ጥፋት፡እንደሚኾን፡ሳያውቅ፥ፍላጻ፡ጕበቱን፡እስኪሰነጥቀው፡ድ ረስ።

24፤ልጆቼ፡ሆይ፥አኹን፡እንግዲህ፡ስሙኝ፡ወደአፌም፡ቃል፡አድምጡኝ።

25፤ልብኽ፡ወደ፡መንገዷ፡አያዘንብል፥በጐዳናዋ፡አትሳት።

26፤ወግታ፡የጣለቻቸው፡ብዙ፡ናቸውና፤ርሷም፡የገደለቻቸው፡እጅግ፡ብዙ፡ናቸው።

27፤ቤቷ፡የሲኦል፡መንገድ፡ነው፤ወደሞት፡ማጀት፡የሚወርድ፡ነው።

__________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡8።_________________

ምዕራፍ፡8፤

1፤በእውኑ፡ጥበብ፡አትጮኽምን፣ማስተዋልስ፡ድምፃን፡አትሰጥምን፣

2፤በኰረብታ፡ላይ፡በመንገድ፡አጠገብ፡በጐዳና፡መካከል፡ትቆማለች።

3፤በበሩ፡አጠገብ፡በከተማዪቱም፡መግቢያ፥በደጁ፡መግቢያ፡ትጮኻለች።

4፤እናንተ፡ሰዎች፥እናንተን፡እጠራለኹ፥ድምፄም፡ወደሰዎች፡ልጆች፡ነው።

5፤እናንተ፡አላዋቂዎች፥ብልኅትን፡አስተውሉ፤እናንተም፡ሰነፎች፡ጥበብን፡በልባችኹ፡ያዙ።

6፤የከበረች፡ነገርን፡እናገራለኹና፡ስሙ፤ከንፈሮቼም፡ቅን፡ነገርን፡ለመናገር፡ይከፈታሉ።

7፤አፌ፡እውነትን፡ይናገራልና፥ከንፈሮቼም፡ክፋትን፡ይጸየፋሉ።

8፤የአፌ፡ቃላት፡ዅሉ፡ጽድቅ፡ናቸው፤ጠማማ፡ዘወርዋራም፡አይደሉም።

9፤እነርሱ፡በሚያስተውሉ፡ዘንድ፡የቀኑ፡ናቸው፥ዕውቀትንም፡ካገኟት፡ሰዎች፡ጋራ፡የተስማሙ፡ናቸው።

10፤ተግሣጼን፡እንጂ፡ብርን፡አትቀበሉ፥ከምዝምዝ፡ወርቅም፡ይልቅ፡ዕውቀትን፡ተቀበሉ።

11፤ጥበብ፡ከቀይ፡ዕንቍ፡ትበልጣለችና፡የከበረ፡ነገር፡ዅሉ፡አይተካከላትም።

12፤እኔ፡ጥበብ፡በብልኅት፡ተቀምጫለኹ፥ዕውቀትንም፡ጥንቃቄንም፡አግኝቻለኹ።

13፤እግዚአብሔርን፡መፍራት፡ክፋትን፡ይጠላል፤ትዕቢትንና፡እብሪትን፡ክፉንም፡መንገድ፡ጠማማውንም፡አፍ፡እጠ ላለኹ።

14፤ምክርና፡መልካም፡ጥበብ፡የእኔ፡ነው፤ማስተዋል፡እኔ፡ነኝ፥ብርታትም፡አለኝ።

15፤ነገሥታት፡በእኔ፡ይነግሣሉ፥ሹማምቶችም፡የቀናውን፡ነገር፡ይደነግጋሉ።

16፤አለቃዎች፡በእኔ፡ያዟሉ፥ከቡራንና፡የምድር፡ፈራጆችም፡ዅሉ።

17፤እኔ፡የሚወዱኝን፡እወዳለኹ፥ተግተው፡የሚሹኝም፡ያገኙኛል።
18፤ብልጥግናና፡ክብር፡በእኔ፡ዘንድ፡ነው፥ብዙ፡ሀብትና፡ጽድቅም።
19፤ፍሬዬም፡ከምዝምዝ፡ወርቅ፡ይሻላል፥ቡቃያዬም፡ከተመረጠች፡ብር።
20፤እኔ፡በጽድቅ፡መንገድ፡እኼዳለኹ፥በፍርድም፡ጐዳና፡መካከል፥
21፤ለሚወዱኝ፡ርስት፡አወርሳቸው፡ዘንድ፡ቤተ፡መዛግብታቸውንም፡እሞላ፡ዘንድ።
22፤እግዚአብሔር፡የመንገዱ፡መዠመሪያ፡አደረገኝ፥በቀድሞ፡ሥራው፡መዠመሪያ።
23፤ከጥንቱ፡ከዘለዓለም፡ዠምሮ፡ተሾምኹ፤ምድር፡ከመፈጠሯ፡አስቀድሞ።
24፤ቀላያት፡ገና፡ሳይኖሩ፡እኔ፡ተወለድኹ፥የውሃ፡ምንጮች፡ገና፡ሳይፈልቁ።
25፤ተራራዎች፡ገና፡ሳይመሠረቱ፥ከኰረብታዎች፡በፊት፡እኔ፡ተወለድኹ፥
26፤ምድሪቱንና፡ሜዳውን፡ገና፡ሳይፈጥር፤የመዠመሪያውን፡የዓለም፡ዐፈር።
27፤ሰማዮችን፡በዘረጋ፡ጊዜ፡ዐብሬ፡ነበርኹ፥በቀላያት፡ፊት፡ክበብን፡በደነገገ፡ጊዜ፥
28፤ደመናትን፡በላይ፡ባዘጋጀ፡ጊዜ፥የቀላይን፡ምንጮች፡ባጸና፡ጊዜ፥
29፤ለባሕርም፡ዳርቻን፡በወሰነ፡ጊዜ፡ውሃ፡ከትእዛዙ፡እንዳያልፍ፥የምድርን፡መሠረት፡በመሠረተ፡ጊዜ፥
30፤የዚያን፡ጊዜ፡እኔ፡በርሱ፡ዘንድ፡ዋና፡ሠራተኛ፡ነበርኹ፤ዕለት፡ዕለት፡ደስ፡አሠኘው፡ነበር፥በፊቱም፡ኹል ጊዜ፡ደስ፡ይለኝ፡ነበር፥
31፤ደስታዬም፡በምድሩ፡ተድላዬም፡በሰው፡ልጆች፡ነበረ።
32፤አኹንም፡ልጆቼ፡ሆይ፥ስሙኝ፤መንገዴንም፡የሚጠብቁ፡ምስጉኖች፡ናቸው።
33፤ትምህርቴን፡ስሙ፥ጠቢባንም፡ኹኑ፥ቸል፡አትበሉትም።
34፤የሚሰማኝ፡ሰው፡ምስጉን፡ነው፡ዕለት፡ዕለት፡በቤቴ፡መግቢያ፡የሚተጋ፥የደጄንም፡መድረክ፡የሚጠብቅ።
35፤እኔን፡ያገኘ፡ሕይወትን፡ያገኛልና፥ከእግዚአብሔርም፡ሞገስን፡ያገኛልና።
36፤እኔን፡ያጣ፡ግን፡ራሱን፡ይጐዳል፤የሚጠሉኝ፡ኹሉ፡ሞትን፡ይወዳሉ።
__________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡9።__________________

ምዕራፍ፡9፤

1፤ጥበብ፡ቤቷን፡ሠራች፥ሰባቱንም፡ምሰሶዎቿን፡አቆመች።
2፤ፍሪዳዋን፡ዐረደች፥የወይን፡ጠጇን፡ደባለቀች፥ማእዷን፡አዘጋጀች።
3፤ባሪያዎቿን፡ልካ፡በከተማዪቱ፡ከፍተኛ፡ስፍራ፡ላይ፡ጠራች፡-
4፤አላዋቂ፡የኾነ፡ወደዚህ፡ፈቀቅ፡ይበል፤አእምሮ፡የጐደላቸውንም፡እንዲህ፡አለች፡-
5፤ኑ፥እንጀራዬን፡ብሉ፥የደባለቅኹትንም፡የወይን፡ጠጅ፡ጠጡ።
6፤አላዋቂነትን፡ትታችኹ፡በሕይወት፡ኑሩ፥በማስተዋልም፡መንገድ፡ኺዱ።
7፤ፌዘኛን፡የሚገሥጽ፡ለራሱ፡ስድብን፡ይቀበላል፥ኃጥእንም፡የሚዘልፍ፡ነውርን፡ያገኛል።
8፤ፌዘኛን፡አትገሥጽ፡እንዳይጠላኽ፤ጠቢብን፡ገሥጽ፡ይወድኽማል።
9፤ለጠቢብ፡ሰው፡ትምህርትን፡ስጠው፥ጥበብንም፡ያበዛል፤ጻድቅንም፡አስተምረው፥ዕውቀትንም፡ያበዛል።
10፤የጥበብ፡መዠመሪያ፡እግዚአብሔርን፡መፍራት፡ነው፤ቅዱሱንም፡ማወቅ፡ማስተዋል፡ነው።
11፤ዘመንኽ፡በእኔ፡ይበዛልና፥የሕይወትኽም፡ዕድሜ፡ይጨመርልኻልና።
12፤ጠቢብ፡ብትኾን፡ለራስኽ፡ጠቢብ፡ትኾናለኽ፥ፌዘኛም፡ብትኾን፡ፌዘኛነትኽን፡ለብቻኽ፡ትሸከማለኽ።
[የሚቀጥለው፡ከግሪክ፡የተጨመረ፡ነው።]፡ልጄ፡ለራስኽ፡ዐዋቂ፡ብትኾን፡ለባልንጀራኽም፡ዐዋቂ፡ትኾናለኽ፤ለራስኽ፡ክፉ፡ ብትኾን፡ግን፡ክፉትኽን፡ትማ ራለኽ።ሐሰትን፡የሚያዘጋጅ፡ሰው፡ነፋሳትን፡እንደሚያዘጋጅ፡ሰው፡ነው፤የሚበሯ፡ወፍንም፡ እንደሚከተል፡ይመ ስላል።የወይኑ፡ቦታ፡መንገዱን፡ተወ፤የሚሠማራባትን፡መንገድ፡ዘነጋ፤ወደ፡ምድረ፡በዳ፡ይኼዳል፡ለጥም፡ ወደተ ሠራች፡አገር፡ይኼዳል፤የማያፈራ፡የማይጠቅም፡ገንዘብንም፡በእጁ፡ይሰበስባል።
13፤ሰነፍ፡ሴት፡ሁከተኛ፡ናት፤ዐሳብ፡የላትም፥አንዳችም፡አታውቅም።
14፤በቤቷ፡ደጅ፡በከተማዪቱ፡ከፍተኛ፡ስፍራ፡በወንበር፡ላይ፡ትቀመጣለች፥

15፤በመንገድ፡የሚያልፉትን፡አካኼዳቸውንም፡ያቀኑትን፡ለመጥራት፦
16፤አላዋቂ፡የኾነ፡ወደዚህ፡ፈቀቅ፡ይበል፤አእምሮ፡የጐደለውንም፡እንዲህ፡አለች፦
17፤የስርቆት፡ውሃ፡ይጣፍጣል፥የተሸሸገም፡እንጀራ፡ደስ፡ያሠኛል።
18፤ነገር፡ግን፥ርሱ፡ሙታን፡ከዚያ፡እንዳሉ፥ዕድምተኛዎቿም፡በሲኦል፡ጥልቀት፡እንዳሉ፡አያውቅም።
_________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡10።________________
ምዕራፍ፡10፤
1፤የሰሎሞን፡ምሳሌዎች።ጠቢብ፡ልጅ፡አባቱን፡ደስ፡ያሠኛል፤ሰነፍ፡ልጅ፡ግን፡ለእናቱ፡ሐዘን፡ነው።
2፤በኀጢአት፡የተገኘ፡መዝገብ፡ጥቅም፡የለውም፤ጽድቅ፡ግን፡ከሞት፡ያድናል።
3፤እግዚአብሔር፡የጻድቁን፡ነፍስ፡አያስርብም፤የኃጥኣንን፡ምኞት፡ግን፡ይገለብጣል።
4፤የታካች፡እጅ፡ችግረኛ፡ታደርጋለች፤የትጉህ፡እጅ፡ግን፡ባለጠጋ፡ታደርጋለች።
5፤በበጋ፡የሚያከማች፡ልጅ፡አስተዋይ፡ነው፤በመከር፡የሚተኛ፡ግን፡ርሱ፡ራሱን፡ያስነውራል።
6፤በረከት፡በጻድቅ፡ራስ፡ላይ፡ነው፤የኃጥኣንን፡አፍ፡ግን፡ግፍ፡ይከድነዋል።
7፤የጻድቅ፡መታሰቢያ፡ለበረከት፡ነው፤የኃጥኣን፡ስም፡ግን፡ይጠፋል።
8፤በልቡ፡ጠቢብ፡የኾነ፡ትእዛዝን፡ይቀበላል፤በከንፈሩ፡የሚሰንፍ፡ግን፡ይወድቃል።
9፤ያለነውር፡የሚኼድ፡ተማምኖ፡ይኼዳል፤መንገዱን፡የሚያጣምም፡ግን፡ይታወቃል።
10፤በዐይኑ፡የሚጠቅስ፡መከራን፡ያመጣል፤ደፍር፡የሚገሥጽ፡ግን፡ሰላምን፡ያደርጋል።
11፤የጻድቅ፡አፍ፡የሕይወት፡ምንጭ፡ናት፤የኃጥኣንን፡አፍ፡ግን፡ግፍ፡ይከድነዋል።
12፤ጥል፡ክርክርን፡ታስነሣለች፤ፍቅር፡ግን፡ኀጢአትን፡ዅሉ፡ትከድናለች።
13፤በብልኀተኛ፡ከንፈር፡ጥበብ፡ትገኛለች፤በትር፡ግን፡አእምሮ፡ለጐደለው፡ሰው፡ዠርባ፡ነው።
14፤ጠቢባን፡ዕውቀትን፡ይሸሽጋሉ፤የሰነፍ፡አፍ፡ግን፡ለጥፋት፡ይቀርባል።
15፤የባለጠጋ፡ሀብት፡ለርሱ፡የጸናች፡ከተማ፡ናት፤የድኻዎች፡ጥፋት፡ድኽነታቸው፡ነው።
16፤የጻድቅ፡ደመ፡ወዝ፡ለሕይወት፡ነው፤የኃጥእ፡ፍሬ፡ግን፡ለኀጢአት፡ነው።
17፤ተግሣጽን፡የሚጠብቅ፡በሕይወት፡መንገድ፡ይኼዳል፤ዘለፋን፡የሚተው፡ግን፡ይስታል።
18፤ጥልን፡የሚከድን፡ሐሰተኛ፡ከንፈር፡አለው፤ሐሜትንም፡የሚገልጥ፡ሰነፍ፡ነው።
19፤በቃል፡ብዛት፡ውስጥ፡ኀጢአት፡ሳይኖር፡አይቀርም፤ከንፈሩን፡የሚገታ፡ግን፡አስተዋይ፡ነው።
20፤የጻድቅ፡ምላስ፡የተፈተነ፡ብር፡ነው፤የኃጥኣን፡ልብ፡ግን፡ምናምን፡ነው።
21፤የጻድቅ፡ከንፈሮች፡ብዙ፡ሰዎችን፡ይመግባሉ፤ሰነፎች፡ግን፡ከልባቸው፡ጕድለት፡የተነሣ፡ይሞታሉ።
22፤የእግዚአብሔር፡በረከት፡ባለጠጋ፡ታደርጋለች፥ሐዘንንም፡ከርሷ፡ጋራ፡አይጨምርም።
23፤ክፉ፡ነገር፡ማድረግ፡ለሰነፍ፡ሰው፡ጨዋታ፡ነው፤እንዲሁም፡ጥበብ፡ለአስተዋይ፡ነው።
24፤የኃጥእ፡ሰው፡ፍርሀት፡በላዩ፡ይመጣበታል፥ለጻድቃንም፡ምኞታቸው፡ትሰጣቸዋለች።
25፤ዐውሎ፡ነፋስ፡ሲያልፍ፡ኃጥእ፡አይገኝም፤ጻድቅ፡ግን፡የዘለዓለም፡መሠረት፡ነው።
26፤ሖምጣጤ፡ጥርስን፥ጢስም፡ዐይንን፡እንደሚጐዳ፥እንዲሁም፡ታካች፡ለላኩት።
27፤እግዚአብሔርን፡መፍራት፡ዘመንን፡ታረዝማለች፤የኃጥኣን፡ዕድሜ፡ግን፡ታጥራለች።
28፤የጻድቃን፡አለኝታ፡ደስታ፡ነው፤የኃጥኣን፡ተስፋ፡ግን፡ይጠፋል።
29፤የእግዚአብሔር፡መንገድ፡ያለነውር፡ለሚኼድ፡ዐምባ፡ነው፥ጥፋት፡ግን፡ክፋትን፡ለሚያደርጉ።
30፤ጻድቃን፡ለዘለዓለም፡አይናወጡም፤ኃጥኣን፡ግን፡በምድር፡ላይ፡አይቀመጡም።
31፤የጻድቅ፡አፍ፡ጥበብን፡ይናገራል፤ጠማማ፡ምላስ፡ግን፡ትቈረጣለች።
32፤የጻድቅ፡ከንፈሮች፡ደስ፡የሚያሠኝ፡ነገርን፡ያውቃሉ፤የኃጥኣን፡አፍ፡ግን፡ጠማማ፡ነው።
_________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡11።________________
ምዕራፍ፡11፤

1፤አባይ፡ሚዛን፡በእግዚአብሔር፡ፊት፡አስጸያፊ፡ነው፤እውነተኛ፡ሚዛን፡ግን፡ደስ፡ያሠኘዋል።
2፤ትዕቢት፡ከመጣች፡ውርደት፡ትመጣለች፤በትሑታን፡ዘንድ፡ግን፡ጥበብ፡ትገኛለች።
3፤ቅኖች፡ቅንነታቸው፡ትመራቸዋለች፤ወስላታዎችን፡ግን፡ጠማማነታቸው፡ታጠፋቸዋለች።
4፤በቍጣ፡ቀን፡ሀብት፡አትረባም፤ጽድቅ፡ግን፡ከሞት፡ታድናለች።
5፤የፍጹም፡ሰው፡ጽድቁ፡መንገዱን፡ያቀናለታል፤ኃጥእ፡ግን፡በኀጢአቱ፡ይወድቃል።
6፤ቅኖችን፡ጽድቃቸው፡ይታደጋቸዋል፤ወስላታዎች፡ግን፡በምኞታቸው፡ይጠመዳሉ።
7፤ኃጥእ፡በሞተ፡ጊዜ፡ተስፋው፡ይቈረጣል፥የኀያል፡አለኝታም፡ይጠፋል።
8፤ጻድቅ፡ከጭንቀት፡ይድናል፥ኃጥእም፡በርሱ፡ፋንታ፡ይመጣል።
9፤ዝንጉ፡ሰው፡በአፉ፡ባልንጀራውን፡ያጠፋል፤ጻድቃን፡ግን፡በዕውቀት፡ይድናሉ።
10፤በጻድቃን፡ልማት፡ከተማ፡ደስ፡ይላታል፥በኃጥኣንም፡ጥፋት፡እልል፡ትላለች።
11፤በቅኖች፡በረከት፡ከተማ፡ከፍ፡ከፍ፡ትላለች፤በኃጥኣን፡አፍ፡ግን፡ትገለበጣለች።
12፤ወዳጁን፡የሚንቅ፡ርሱ፡አእምሮ፡የጐደለው፡ነው፤አስተዋይ፡ግን፡ዝም፡ይላል።
13፤ለሐሜት፡የሚኼድ፡ምስጢሩን፡ይገልጣል፤በመንፈስ፡የታመነ፡ግን፡ነገሩን፡ይሰውራል።
14፤መልካም፡ምክር፡ከሌለ፡ዘንድ፡ሕዝብ፡ይወድቃል፤በመካሮች፡ብዛት፡ግን፡ደኅንነት፡ይኾናል።
15፤ለማያውቅ፡የሚዋስ፡ክፉ፡መከራን፡ይቀበላል፤ዋስነትን፡የሚጠላ፡ግን፡ይድናል።
16፤ሞገስ፡ያላት፡ሴት፡ክብርን፡ታገኛለች፥ሀኬተኛዎችም፡ሀብትን፡ያገኛሉ።
17፤ቸር፡ሰው፡ለራሱ፡መልካም፡ያደርጋል፤ጨካኝ፡ግን፡ሥጋውን፡ይጐዳል።
18፤የኃጥእ፡ሰው፡ሞያ፡ሐሰተኛ፡ነው፤ጽድቅን፡የሚዘራ፡ግን፡የታመነ፡ዋጋ፡አለው።
19፤በጽድቅ፡የሚጸና፡በሕይወት፡ይኖራል፤ክፋትን፡የሚከተል፡ግን፡ለሞቱ፡ነው።
20፤ልበ፡ጠማማዎች፡በእግዚአብሔር፡ዘንድ፡አስጸያፊዎች፡ናቸው፤በመንገዳቸው፡ፍጹማን፡የኾኑ፡ግን፡የተወደዱ ፡ናቸው።
21፤ክፉ፡ሰው፡እጅ፡በእጅ፡ሳይቀጣ፡አይቀርም፤የጻድቃን፡ዘር፡ግን፡ይድናል።
22፤የወርቅ፡ቀለበት፡በዕሪያ፡አፍንጫ፡እንደ፡ኾነ፥ከጥበብ፡የተለየች፡ቈንጆ፡ሴትም፡እንዲሁ፡ናት።
23፤የጻድቃን፡ምኞት፡በጎ፡ብቻ፡ነው፤የኃጥኣን፡ተስፋ፡ግን፡መቅሠፍት፡ነው።
24፤ያለውን፡የሚበትን፡ሰው፡አለ፥ይጨመርለታልም፤ያለቅጥ፡የሚነፍግ፡ሰውም፡አለ፥ይደኸያልም።
25፤የምትባረክ፡ነፍስ፡ትጠግባለች፥የረካም፡ርሱ፡ደግሞ፡ይረካል።
26፤እኽልን፡የሚያስቀር፡ሰው፡በሕዝብ፡ዘንድ፡ይረገማል፤በረከት፡ግን፡በሚሸጠው፡ራስ፡ላይ፡ነው።
27፤መልካምን፡ተግቶ፡የሚሻ፡ደስታን፡ይፈልጋል፤ክፉን፡በሚፈልግ፡ግን፡ክፉ፡ይመጣበታል።
28፤በባለጠግነቱ፡የሚተማመን፡ሰው፡ይወድቃል፡ጻድቃን፡ግን፡እንደ፡ቅጠል፡ይለመልማሉ።
29፤ቤቱን፡የሚያውክ፡ሰው፡ነፋስን፡ይወርሳል፥ሰነፍም፡ለጠቢብ፡ተገዢ፡ይኾናል።
30፤የጻድቅ፡ፍሬ፡የሕይወት፡ዛፍ፡ናት፥ነፍሶችንም፡የሚሰበስብ፡ርሱ፡ጠቢብ፡ነው።
31፤እንሆ፥ጻድቅ፡በምድር፡ላይ፡ፍዳውን፡የሚቀበል፡ከኾነ፥ይልቁንስ፡ኃጥእና፡ዐመፀኛ፡እንዴት፡ይኾናሉ!

____________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡12።___________________

ምዕራፍ፡12፤

1፤ተግሣጽን፡የሚወድ፡ዕውቀትን፡ይወዳል፤ዘለፋን፡የሚጠላ፡ግን፡ደንቈሮ፡ነው።
2፤ደጎና፡ሰው፡ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ሞገስን፡ያገኛል፤ተንኰለኛውን፡ሰው፡ግን፡ይቀሥፈዋል።
3፤ሰውን፡ዐመፃ፡አያጸናውም፤የጻድቃን፡ሥር፡ግን፡አይንቀሳቀስም።
4፤ልባም፡ሴት፡ለባሏ፡ዘውድ፡ናት፤አሳፋሪ፡ሴት፡ግን፡በዐጥንቱ፡ውስጥ፡እንደ፡ቅንቅን፡ናት።
5፤የጻድቃን፡ዐሳብ፡ቅን፡ነው፤የኃጥኣን፡ምክር፡ግን፡ተንኰል፡ነው።
6፤የኃጥኣን፡ቃል፡ደምን፡ለማፍሰስ፡ትሸምቃለች፤የቅኖች፡አፍ፡ግን፡ይታደጋቸዋል።
7፤ኃጥኣን፡ይገለበጣሉ፥ደግሞም፡አይገኙም፤የጻድቃን፡ቤት፡ግን፡ጸንቶ፡ይኖራል።

8፤ሰው፡በጥበቡ፡ይመሰገናል፤ልቡ፡ጠማማ፡የኾነ፡ሰው፡ግን፡ይናቃል።
9፤ለራሱ፡ባሪያ፡ኾኖ፡የተጠቃ፡ሰው፡እንጀራ፡ጐድሎት፡ራሱን፡ካከበረው፡ሰው፡ይሻላል።
10፤ጻድቅ፡ሰው፡ለእንስሳው፡ነፍስ፡ይራራል፤የኃጥኣን፡ምሕረት፡ግን፡ጨካኝ፡ነው።
11፤ምድሩን፡የሚሠራ፡ሰው፡እንጀራ፡ይጠግባል፤ለከንቱ፡ነገር፡የሚሮጥ፡ግን፡አእምሮ፡የጐደለው፡ነው።
12፤የኃጥኣን፡ፈቃድ፡የክፉዎች፡ወጥመድ፡ናት፤የጻድቃን፡ሥር፡ግን፡ፍሬን፡ያፈራል።
13፤ክፉ፡ሰው፡በከንፈሩ፡ኀጢአት፡ይጠመዳል፤ጻድቅ፡ግን፡ከመከራ፡ያመልጣል።
14፤የሰው፡ነፍስ፡ከአፉ፡ፍሬ፡መልካም፡ነገርን፡ትጠግባለች፥ሰውም፡እንደ፡እጁ፡ሥራ፡ዋጋውን፡ይቀበላል።
15፤የሰነፍ፡መንገድ፡በዐይኑ፡የቀናች፡ናት፤ጠቢብ፡ግን፡ምክርን፡ይሰማል።
16፤የሰነፍ፡ቍጣ፡ቶሎ፡ይታወቃል፤ብልኅ፡ሰው፡ግን፡ነውርን፡ይሰውራል።
17፤እውነተኛን፡ነገር፡የሚናገር፡ቅን፡ነገርን፡ያወራል፤የሐሰት፡ምስክር፡ግን፡ተንኰልን፡ያወራል።
18፤እንደሚዋጋ፡ሰይፍ፡የሚለፈልፍ፡ሰው፡አለ፤የጠቢባን፡ምላስ፡ግን፡ጤና፡ነው።
19፤የእውነት፡ከንፈር፡ለዘለዓለም፡ትቆማለች፤ውሸተኛ፡ምላስ፡ግን፡ለቅጽበት፡ነው።
20፤ክፉን፡በሚያስቡ፡ልብ፡ውስጥ፡ተንኰል፡አለ፤በሰላም፡ለሚመክሩ፡ግን፡ደስታ፡አላቸው።
21፤ጻድቅን፡መከራ፡አያገኘውም፤ኃጥኣን፡ግን፡ክፋትን፡የተሞሉ፡ናቸው።
22፤ውሸተኛ፡ከንፈር፡በእግዚአብሔር፡ዘንድ፡አስጸያፊ፡ነው፤እውነትን፡የሚያደርጉ፡ግን፡በርሱ፡ዘንድ፡የተወ ደዱ፡ናቸው።
23፤ብልኅ፡ሰው፡ዕውቀትን፡ይሸሽጋል፤የሰነፎች፡ልብ፡ግን፡ስንፍናን፡ያወራል።
24፤የትጉህ፡እጅ፡ትገዛለች፤የታካች፡እጅ፡ግን፡ትገብራለች።
25፤ሰውን፡የልቡ፡ሐዘን፡ያዋርደዋል፤መልካም፡ቃል፡ግን፡ደስ፡ያሠኘዋል።
26፤ጻድቅ፡ለባልንጀራው፡መንገዱን፡ያሳያል፤የኃጥኣን፡መንገድ፡ግን፡ታስታቸዋለች።
27፤ታካች፡ሰው፡አደን፡ምንም፡አያድንም፤ለሰው፡የከበረ፡ሀብት፡ትጋት፡ነው።
28፤በጽድቅ፡መንገድ፡ላይ፡ሕይወት፡አለ፡በጐዳናዋም፡ሞት፡የለም።
__________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡13።________________
ምዕራፍ፡13፤
1፤ባላእምሮ፡ልጅ፡የአባቱን፡ተግሣጽ፡ይሰማል።ፌዘኛ፡ግን፡ተግሣጽን፡አይሰማም።
2፤ሰው፡ከአፉ፡ፍሬ፡መልካምን፡ይበላል፤የዐመፀኞች፡ነፍስ፡ግን፡ግፍን፡ትሻለች።
3፤አፉን፡የሚጠብቅ፡ነፍሱን፡ይጠብቃል፤ከንፈሩን፡የሚያሞጠሙጥ፡ግን፡ጥፋትን፡ያገኘዋል።
4፤የታካች፡ሰው፡ነፍስ፡ትመኛለች፤አንዳችም፡አታገኝም፤የትጉህ፡ነፍስ፡ግን፡ትጠግባለች።
5፤ጻድቅ፡ሐሰትን፡ይጠላል፤ኃጥእ፡ግን፡ያሳፍራል፡ያስነውራልም።
6፤በመንገዱ፡ያለነውር፡የሚኼደውን፡ጽድቅ፡ይጠብቀዋል፤ኀጢአት፡ግን፡ኀጢአተኛውን፡ይጥለዋል።
7፤ራሱን፡ባለጠጋ፡የሚያስመስል፡ሰው፡አለ፥ነገር፡ግን፥አንዳች፡የለውም፤ራሱን፡ድኻ፡የሚያስመስል፡አለ፥ነገ ር፡ግን፥እጅግ፡ባለጠግነት፡አለው።
8፤ለሰው፡ነፍስ፡ቤዛው፡ሀብቱ፡ነው፤ድኻ፡ግን፡ተግሣጽን፡አይሰማም።
9፤ዅልጊዜ፡ለጻድቃን፡ብርሃን፡ነው፤የኃጥኣን፡መብራት፡ግን፡ይጠፋል።
10፤በትዕቢት፡ጠብ፡ብቻ፡ይኾናል፤ጥበብ፡ግን፡ምክርን፡በሚቀበሉ፡ዘንድ፡ናት።
11፤በችኰላ፡የምትከማች፡ሀብት፡ትጐድላለች፤ጥቂት፡በጥቂት፡የተከማቸች፡ግን፡ትበዛለች።
12፤የምትዘገይ፡ተስፋ፡ልብን፡ታሳዝናለች፤የተገኘች፡ፈቃድ፡ግን፡የሕይወት፡ዛፍ፡ናት።
13፤ትእዛዝን፡የሚያቃልል፡በትእዛዝ፡ተይዞ፡ይጠፋል፤ትእዛዝን፡የሚፈራ፡ግን፡በደኅንነት፡ይኖራል።
14፤ሰው፡ከሞት፡ወጥመድ፡ያመልጥ፡ዘንድ፡የጠቢብ፡ሰው፡ትምህርት፡የሕይወት፡ምንጭ፡ነው።
15፤መልካም፡ዕውቀት፡ሞገስን፡ይሰጣል፤የወስላታዎች፡መንገድ፡ግን፡ሻካራ፡ናት።
16፤ብልኅ፡ዅሉ፡በዕውቀት፡ይሠራል፤ሰነፍ፡ግን፡ስንፍናውን፡ይገልጣል።

17፤መጥፎ፡መልእክተኛ፡በክፉ፡ላይ፡ይወድቃል፤የታመነ፡መልእክተኛ፡ግን፡ፈውስ፡ነው።
18፤ድኽነትና፡ነውር፡ተግሣጽን፡ቸል፡ለሚሉ፡ነው፤ዘለፋን፡የሚሰማ፡ግን፡ይከብራል።
19፤የተፈጸመች፡ፈቃድ፡ሰውነትን፡ደስ፡ታሠኛለች፤ሰነፎች፡ግን፡ከክፉ፡መራቅን፡ይጸየፋሉ።
20፤ከጠቢባን፡ጋራ፡የሚኼዱ፡ጠቢብ፡ይኾናል፤የሰነፎች፡ባልንጀራ፡ግን፡ክፉ፡መከራን፡ይቀበላል።
21፤ክፉ፡ነገር፡ኀጢአተኛዎችን፡ያሳድዳቸዋል፤ጻድቃን፡ግን፡መልካሙን፡ዋጋ፡ይቀበላሉ።
22፤ጻድቅ፡ሰው፡ለልጅ፡ልጆቹ፡ያወርሳል፤የኀጢአተኛ፡ብልጥግና፡ግን፡ለጻድቅ፡ትጠበቃለች።
23፤በድኻዎች፡ዕርሻ፡ላይ፡ብዙ፡ሲሳይ፡አለ፤ከፍርድ፡መጓደል፡የተነሣ፡ግን፡ይጠፋል።
24፤በበትር፡ከመምታት፡የሚራራ፡ሰው፡ልጁን፡ይጠላል፤ልጁን፡የሚወድ፡ግን፡ተግቶ፡ይገሥጸዋል።
25፤ጻድቅ፡ሰውነቱ፡እስክትጠግብ፡ድረስ፡ይበላል፤የኃጥኣን፡ሆድ፡ግን፡ይራባል።
__________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡14።__________________
ምዕራፍ፡14፤
1፤ብልኀተኛ፡ሴት፡ቤቷን፡ትሠራለች፤ሰነፍ፡ሴት፡ግን፡በእጇ፡ታፈርሰዋለች።
2፤በቅን፡የሚኼድ፡ሰው፡እግዚአብሔርን፡ይፈራል፤መንገዱን፡የሚያጣምም፡ግን፡ይንቀዋል።
3፤በሰነፍ፡አፍ፡የትዕቢት፡በትር፡አለ፤የጠቢባን፡ከንፈር፡ግን፡ትጠብቃቸዋለች።
4፤በሬ፡በሌለበት፡ስፍራ፡እኽል፡አይገኝም፤ብዙ፡ሲሳይ፡ግን፡በበሬዎች፡ኀይል፡ነው።
5፤የታመነ፡ምስክር፡አይዋሽም፤የሐሰት፡ምስክር፡ግን፡በሐሰት፡ይናገራል።
6፤ፌዘኛ፡ሰው፡ጥበብን፡ይፈልጋል፡አያገኛትም፤ለአስተዋይ፡ግን፡ዕውቀትን፡ማግኘት፡አያስቸግረውም።
7፤ከሰነፍ፡ሰው፡ፊት፡ራቅ፥በርሱ፡ዘንድ፡የዕውቀትን፡ከንፈር፡አታገኝምና።
8፤የብልኀ፡ሰው፡ጥበብ፡መንገዱን፡ያስተውል፡ዘንድ፡ነው፤የሰነፎች፡ስንፍና፡ግን፡ሽንገላ፡ነው።
9፤ሰነፉ፡በኀጢአት፡ያፌዛል፤በቅኖች፡መካከል፡ግን፡ቸርነት፡አለች።
10፤የራሱን፡ሐዘን፡ልብ፡ያውቃል፤ከደስታውም፡ጋራ፡ሌላ፡ሰው፡አይገናኝም።
11፤የኃጥኣን፡ቤት፡ይፈርሳል፤የቅኖች፡ማደሪያ፡ግን፡ያብባል።
12፤ለሰው፡ቅን፡የምትመስል፡መንገድ፡አለች፡ፍጻሜዋ፡ግን፡የሞት፡መንገድ፡ነው።
13፤በሣቅ፡ደግሞ፡ልብ፡ያዝናል፥የደስታም፡ፍጻሜ፡ልቅሶ፡ነው።
14፤ልቡን፡ከጽድቅ፡የሚመልስ፡ሰው፡ከመንገዱ፡ፍሬ፡ይጠግባል፥ጻድቅም፡ሰው፡ደግሞ፡በራሱ።
15፤የዋህ፡ቃልን፡ዅሉ፡ያምናል፤ብልኀ፡ግን፡አካኼዱን፡ይመለከታል።
16፤ጠቢብ፡ሰው፡ይፈራል፡ከክፉም፡ይሸሻል፤ሰነፍ፡ግን፡ራሱን፡ታምኖ፡ይኰራል።
17፤ቍጡ፡ሰው፡በስንፍና፡ይሠራል፤አስተዋይ፡ግን፡ይታገሣል።
18፤አላዋቂዎች፡ሰዎች፡ስንፍናን፡ይወርሳሉ፤ብልኀኖች፡ግን፡ዕውቀትን፡እንደ፡ዘውድ፡ይጭናሉ።
19፤ኀጢአተኛዎች፡በደጎች፡ፊት፡ይጐነበሳሉ፥ኃጥኣንም፡በጻድቃን፡በር።
20፤ድኻ፡በባልንጀራው፡ዘንድ፡የተጠላ፡ነው፡የባለጠጋ፡ወዳጆች፡ግን፡ብዙዎች፡ናቸው።
21፤ባልንጀራውን፡የሚንቅ፡ይበድላል፡ለድኻ፡ግን፡የሚራራ፡ምስጉ፡ነው።
22፤ክፉ፡የሚያደርጉ፡ይስታሉ፤ምሕረትና፡እውነት፡ግን፡መልካምን፡ለሚያደርጉ፡ናቸው።
23፤በድካም፡ዅሉ፡ልምላሜ፡ይገኛል፤ብዙ፡ነገር፡በሚናገር፡ከንፈር፡ግን፡ድኽነት፡ብቻ፡አለ።
24፤የጠቢባን፡ዘውድ፡ባለጠግነታቸው፡ነው፤የሰነፎች፡ስንፍና፡ግን፡ስንፍና፡ነው።
25፤እውነተኛ፡ምስክር፡ነፍሶችን፡ያድናል፤በሐሰት፡የሚናገር፡ግን፡ሸንጋይ፡ነው።
26፤እግዚአብሔርን፡ለሚፈራ፡ጠንካራ፡መታመን፡አለው፥ለልጆቹም፡መጠጊያ፡ይኖራል።
27፤ሰው፡ከሞት፡ወጥመድ፡ያመልጥ፡ዘድን፡እግዚአብሔርን፡መፍራት፡የሕይወት፡ምንጭ፡ነው።
28፤የንጉሥ፡ክብር፡በሕዝብ፡ብዛት፡ነው፤በሰው፡ጥቂትነት፡ግን፡የገዢ፡ጥፋት፡አለ።
29፤ለትግሥተኛ፡ሰው፡ብዙ፡ማስተዋል፡አለው፤ቍጡ፡ግን፡ስንፍናውን፡ከፍ፡ከፍ፡ያደርጋል።

30፤ትሑት፡ልብ፡የሥጋ፡ሕይወት፡ነው፤ቅንአት፡ግን፡ዐጥንትን፡ያነቅዛል።
31፤ድኻን፡የሚያስጨንቅ፡ፈጣሪውን፡ይሰድባል፤ለድኻ፡ምሕረትን፡የሚያደርግ፡ግን፡ያከብረዋል።
32፤ኃጥእ፡በክፋቱ፡ይደፋል፤ጻድቅ፡ግን፡በእውነቱ፡ይታመናል።
33፤በዐዋቂ፡ልብ፡ጥበብ፡ትቀመጣለች፤በሰነፎች፡ውስጥ፡ግን፡አትታወቅም።
34፤ጽድቅ፡ሕዝብን፡ከፍ፡ከፍ፡ታደርጋለች፤ኀጢአት፡ግን፡ሕዝብን፡ታስነውራለች።
35፤አስተዋይ፡አገልጋይ፡በንጉሥ፡ዘንድ፡ይወደዳል፤በሚያሳፍር፡ላይ፡ግን፡ቍጣው፡ይኾናል።
__________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡15።________________
ምዕራፍ፡15፤
1፤የለዘበች፡መልስ፡ቍጣን፡ትመልሳለች፡ሻካራ፡ቃል፡ግን፡ቍጣን፡ታስነሣለች።
2፤የጠቢባን፡ምላስ፡ዕውቀትን፡ያሳምራል፤የሰነፎች፡አፍ፡ግን፡ስንፍናን፡ያፈልቃል።
3፤የእግዚአብሔር፡ዐይኖች፡በስፍራ፡ዅሉ፡ናቸው፤ክፉዎችንና፡ደጎችን፡ይመለከታሉ።
4፤ፈዋሽ፡ምላስ፡የሕይወት፡ዛፍ፡ነው፤የጠማማ፡ምላስ፡ግን፡ነፍስን፡ይሰብራል።
5፤ሰነፍ፡የአባቱን፡ተግሣጽ፡ይንቃል፤ዘለፋን፡የሚቀበል፡ግን፡አእምሮው፡የበዛ፡ነው።
6፤በጻድቅ፡ሰው፡ቤት፡ብዙ፡ኀይል፡አለ፤የኃጥእ፡ሰው፡መዝገብ፡ግን፡ሁከት፡ነው።
7፤የጠቢባን፡ከንፈር፡ዕውቀትን፡ትዘራለች፤የሰነፎች፡ልብ፡ግን፡እንዲህ፡አይደለም።
8፤የኃጥኣን፡መሥዋዕት፡በእግዚአብሔር፡ዘንድ፡አስጸያፊ፡ነው፤የቅኖች፡ጸሎት፡ግን፡በርሱ፡ዘንድ፡የተወደደ፡ ነው።
9፤የኃጥኣን፡መንገድ፡በእግዚአብሔር፡ዘንድ፡አስጸያፊ፡ነው፤ርሱ፡ግን፡ጽድቅን፡የሚከተል፡ይወዷል።
10፤ክፉ፡መቅሠፍት፡መንገድን፡በተወ፡ሰው፡ላይ፡ይመጣል፥ዘለፋንም፡የሚጠላ፡ይሞታል።
11፤ሲኦልና፡ጥፋት፡በእግዚአብሔር፡ፊት፡የታወቁ፡ናቸው፤ይልቁንም፡የሰዎች፡ልብ፡የታወቀ፡ነው።
12፤ፌዘኛ፡ሰው፡የሚዘልፈውን፡አይወድም፥ወደ፡ጠቢባንም፡አይኼድም።
13፤ደስ፡ያለው፡ልብ፡ፊትን፡ያበራል፤በልብ፡ሐዘን፡ግን፡ነፍስ፡ትሰበራለች።
14፤የዐዋቂ፡ልብ፡ዕውቀትን፡ይፈልጋል፤የሰነፎች፡አፍ፡ግን፡በስንፍና፡ይሰማራል።
15፤ልቡ፡የሚያዝን፡ሰው፡ዘመኑ፡ዅሉ፡የከፉች፡ናት፤የልብ፡ደስታ፡ግን፡ዅልጊዜ፡እንደ፡ግብዣ፡ነው።
16፤እግዚአብሔርን፡ከመፍራት፡ጋራ፡ያለ፡ጥቂት፡ነገር፡ሁከት፡ካለበት፡ከብዙ፡መዝገብ፡ይሻላል።
17፤የጐመን፡ወጥ፡በፍቅር፡መብላት፡የሰባ፡ፍሪዳን፡ጥል፡ባለበት፡ዘንድ፡ከመብላት፡ይሻላል።
18፤ቍጡ፡ሰው፡ጠብን፡ያነሣሣል፤ትዕግሥተኛ፡ሰው፡ግን፡ጸጥ፡ያሠኘዋል።
19፤የታካች፡መንገድ፡እንደ፡ሾኽ፡ዐጥር፡ናት፤የጻድቃን፡መንገድ፡ግን፡የተደላደለች፡ናት።
20፤ጠቢብ፡ልጅ፡አባቱን፡ደስ፡ያሠኛል፤ሰነፍ፡ልጅ፡ግን፡እናቱን፡ይንቃል።
21፤ልብ፡ለሌለው፡ሰው፡ስንፍና፡ደስታ፡ናት፤አስተዋይ፡ግን፡አካኼዱን፡ያቀናል።
22፤ምክር፡ከሌለች፡ዘንድ፡የታሰበው፡ሳይሳካ፡ይቀራል፤መካሮች፡በበዙበት፡ዘንድ፡ግን፡ይጸናል።
23፤ሰው፡በአፉ፡መልስ፡ደስ፡ይለዋል፤ቃልም፡በጊዜው፡ምንኛ፡መልካም፡ነው!
24፤በታች፡ካለው፡ከሲኦል፡ያመልጥ፡ዘንድ፡የሕይወት፡መንገድ፡አስተዋዩን፡ሰው፡ወደ፡ላይ፡ይወስደዋል።
25፤እግዚአብሔር፡የትዕቢተኛዎች፡ቤት፡ይነቅላል፤የባልቴትን፡ዳርቻ፡ግን፡ያጸናል።
26፤የበደለኛ፡ዐሳብ፡በእግዚአብሔር፡ዘንድ፡አስጸያፊ፡ናት፤ያማረ፡ቃል፡ግን፡ጥሩ፡ነው።
27፤ትርፍ፡ለማግኘት፡የሚሣሣ፡ሰው፡የራሱን፡ቤት፡ያውካል፤መማለጃን፡የሚጠላ፡ግን፡በሕይወት፡ይኖራል።
28፤የጻድቅ፡ልብ፡መልሱን፡ያስባል፡የኃጥኣን፡አፍ፡ግን፡ክፋትን፡ያፈልቃል።
29፤እግዚአብሔር፡ከኃጥኣን፡ይርቃል፤የጻድቃንን፡ጸሎት፡ግን፡ይሰማል።
30፤የዐይን፡ብርሃን፡ልብን፡ደስ፡ያሠኛል፥መልካም፡ወሬም፡ዐጥንትን፡ያለመልማል።
31፤የሕይወትን፡ተግሣጽ፡የሚሰማ፡ጆሮ፡በጠቢባን፡መካከል፡ይኖራል።
32፤ተግሣጽን፡ቸል፡የሚል፡የራሱን፡ነፍስ፡ይንቃል፤ዘለፋን፡የሚሰማ፡ግን፡አእምሮ፡ያገኛል።

33፤እግዚአብሔርን፡መፍራት፡የጥበብ፡ትምህርት፡ነው፤ትሕትናም፡ክብረትን፡ትቀድማለች።

_________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡16።________________

ምዕራፍ፡16፤

1፤የልብ፡መዘጋጀት፡ከሰው፡ነው፤የምላስ፡መልስ፡ግን፡ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ነው።

2፤የሰው፡መንገድ፡ዅሉ፡በዐይኖቹ፡ፊት፡ንጹሕ፡ነው፤እግዚአብሔር፡ግን፡መንፈስን፡ይመዝናል።

3፤ሥራኽን፡ለእግዚአብሔር፡ዐደራ፡ስጥ፥ዐሳብኽም፡ትጸናለች።

4፤እግዚአብሔር፡ዅሉን፡ለርሱ፡ለራሱ፡ፈጠረ፥ኃጥኡን፡ደግሞ፡ለክፉ፡ቀን።

5፤በልቡ፡የታበየ፡ዅሉ፡በእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ርኩስ፡ነው፥እጅ፡በእጅም፡ሳይቀጣ፡አይቀርም።

6፤በምሕረትና፡በእውነት፡ኀጢአት፡ትሰረያለች፥እግዚአብሔርንም፡በመፍራት፡ሰው፡ከክፋት፡ይመለሳል።

7፤የሰው፡አካኼድ፡እግዚአብሔርን፡ደስ፡ያሠኘው፡እንደ፡ኾነ፤በርሱና፡በጠላቶቹ፡መካከል፡ስንኳ፡ሰላምን፡ያደ ርጋል።

8፤በጽድቅ፡የሚገኝ፡ጥቂት፡ነገር፡በዐመፅ፡ከሚገኝ፡ከብዙ፡ትርፍ፡ይሻላል።

9፤የሰው፡ልብ፡መንገዱ፡ያዘጋጃል፤እግዚአብሔር፡ግን፡አካኼዱን፡ያቀናለታል።

10፤የእግዚአብሔር፡ብይን፡በንጉሥ፡አፍ፡ነው፥አፉም፡በፍርድ፡አይስትም።

11፤እውነተኛ፡ሚዛንና፡መመዘኛ፡የእግዚአብሔር፡ናቸው፤የከረጢት፡መመዘኛዎች፡ዅሉ፡የርሱ፡ሥራ፡ናቸው።

12፤ግፍን፡መሥራት፡በንጉሥ፡ዘንድ፡ጸያፍ፡ነገር፡ነው፥ዙፋን፡በጽድቅ፡ይጸናልና።

13፤የጽድቅ፡ከንፈር፡የነገሥታት፡ደስታ፡ናት፥በቅን፡የሚናገር፡ርሱንም፡ይወዱታል።

14፤የንጉሥ፡ቍጣ፡እንደ፡ሞት፡መልእክተኛ፡ነው፤ጠቢብ፡ሰው፡ግን፡ያቈላምጠዋል።

15፤በንጉሥ፡ፊት፡ብርሃን፡ዘንድ፡ሕይወት፡አለ፥መልካም፡ፈቃዱም፡እንደ፡በልግ፡ዝናብ፡ደመና፡ነው።

16፤ጥበብን፡ማግኘት፡ምንኛ፡ከወርቅ፡ይሻላል! ማስተዋልንም፡ማግኘት፡ከብር፡ይልቅ፡የሚመረጥ፡ነው።

17፤የቅኖች፡መንገድ፡ከክፋት፡መራቅ፡ነው፤መንገዱን፡የሚጠብቅ፡ነፍሱን፡ይጠብቃታል።

18፤ትዕቢት፡ጥፋትን፥ኵሩ፡መንፈስም፡ውድቀትን፡ይቀድማል።

19፤ከዕቡያን፡ጋራ፡ምርኮ፡ከመካፈል፥ከትሑታን፡ጋራ፡በተዋረደ፡መንፈስ፡መኾን፡ይሻላል።

20፤ቃልን፡የሚያዳምጥ፡መልካም፡ነገርን፡ያገኛል፤በእግዚአብሔር፡የታመነ፡ምስጉን፡ነው።

21፤ልቡ፡ጠቢብ፡የኾነ፡አስተዋይ፡ይባላል፥በከንፈሩም፡ጣፋጭ፡የኾነ፡ትምህርትን፡ያበዛል።

22፤ገንዘብ፡ላደረገው፡ሰው፡ዕውቀት፡የሕይወት፡ምንጭ፡ነው፤ስንፍና፡ግን፡የሰነፎች፡ቅጣት፡ነው።

23፤የጠቢብ፡ልብ፡አፉን፡ያስተምራል፥ለከንፈሩም፡ትምህርትን፡ይጨምራል።

24፤ያማረ፡ቃል፡የማር፡ወለላ፡ነው፤ለነፍስ፡ጣፋጭ፡ለዐጥንትም፡ጤና፡ነው።

25፤ለሰው፡ቅን፡የምትመስል፡መንገድ፡አለች፤ፍጻሜዋ፡ግን፡የሞት፡መንገድ፡ነው።

26፤የሠራተኛ፡ራብ፡ለርሱ፡ይሠራል፥አፉ፡ይጐተጕተዋልና።

27፤ምናምንቴ፡ሰው፡ክፋትን፡ይምሳል፥በከንፈሩም፡የሚቃጠል፡እሳት፡አለ።

28፤ጠማማ፡ሰው፡ጥልን፡ይዘራል፤ዦሮ፡ጠቢ፡ሰው፥የተማመኑትን፡ወዳጆች፡ይለያያል።

29፤ግፈኛ፡ሰው፡ወዳጁን፡ያባብላል፥መልካምም፡ወዳይደለ፡መንገድ፡ይመራዋል።

30፤ዐይኑን፡የሚዘጋ፡ጠማማ፡ዐሳብን፡ያስባል፤ከንፈሩን፡የሚነክስ፡ክፋትን፡ይፈጽማል።

31፤የሸበተ፡ጠጕር፡የክብር፡ዘውድ፡ነው፥ርሱም፡በጽድቅ፡መንገድ፡ይገኛል።

32፤ትዕግሥተኛ፡ሰው፡ከኀያል፡ሰው፡ይሻላል፥በመንፈሱም፡ላይ፡የሚገዛ፡ከተማ፡ከሚወስዱ፡ይበልጣል።

33፤ዕጣ፡በጕያ፡ይጣላል፤መደቧ፡ዅሉ፡ግን፡ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ነው።

_________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡17።________________

ምዕራፍ፡17፤

1፤ጥል፡ባለበት፡ዘንድ፡ዕርድ፡ከሞላበት፡ቤት፡በጸጥታ፡ደረቅ፡ቍራሽ፡ይሻላል።

2፤አስተዋይ፡ባሪያ፡ነውረኛውን፡ልጅ፡ይገዛል፥በወንድማማች፡መካከልም፡ርስትን፡ይካፈላል።

3፤ማቅለጫ፡ለብር፥ከውር፡ለወርቅ፡ነው፤እግዚአብሔር፡ግን፡ልብን፡ይፈትናል።
4፤ክፉ፡ሰው፡የበደለኛን፡ከንፈር፡ይሰማል፤ሐሰተኛም፡ወደ፡ተንኰለኛ፡ምላስ፡ያደምጣል።
5፤በድኻ፡የሚያላግጥ፡ፈጣሪውን፡ይሰድባል፤በጥፋትም፡ደስ፡የሚለው፡ሳይቀጣ፡አይቀርም።
6፤የሽማግሌዎች፡አክሊል፡የልጅ፡ልጆች፡ናቸው፤የልጆችም፡ክብር፡አባቶቻቸው፡ናቸው።
7፤ለሰነፍ፡የኵራት፡አነጋገር፡አይገባውም፤ይልቁንም፡ሐሰተኛ፡ከንፈር፡ለመኰንን፡አይገባውም።
8፤ገንዘብ፡ባደረገው፡ፊት፡መማለጃ፡እንደ፡ተዋበ፡ዕንቍ፡ነው፥ወደ፡ዞረበትም፡ስፍራ፡ኹሉ፡ሥራውን፡ያቀናል።
9፤ኀጢአትን፡የሚከድን፡ሰው፡ፍቅርን፡ይሻል፤ነገርን፡የሚደጋግም፡ግን፡የተማመኑትን፡ወዳጆቹን፡ይለያያል።
10፤መቶ፡ግርፋት፡በሰነፍ፡ጠልቆ፡ከሚገባ፡ይልቅ፡ተግሣጽ፡በአስተዋይ፡ሰው፡ጠልቆ፡ወደ፡ልቡ፡ይገባል።
11፤ክፉ፡ሰው፡ዐመፃን፡ብቻ፡ይሻል፤ስለዚህ፥ጨካኝ፡መልአክ፡ይላክበታል።
12፤ሰነፍን፡በስንፍናው፡ከመገናኘት፡ልጆቿ፡የተነጠቁባትን፡ድብ፡መገናኘት፡ይሻላል።
13፤በመልካም፡ፋንታ፡ክፉን፡የሚመልስ፥ክፉ፡ነገር፡ከቤቱ፡አትርቅም።
14፤የጠብ፡መዠመሪያ፡እንደ፡ውሃ፡አፈሳሰስ፡ነው፤ስለዚህ፥ጠብ፡ሳይበረታ፡አንተ፡ክርክርን፡ተው።
15፤ኃጥኡን፡የሚያጸድቅና፡በጻድቁ፡ላይ፡የሚፈርድ፥ኹለቱ፡በእግዚአብሔር፡ዘንድ፡አስጸያፊዎች፡ናቸው።
16፤በሰነፍ፡እጅ፡የጥበብ፡መግዣ፡ገንዘብ፡መኖሩ፡ስለ፡ምንድር፡ነው፤ጥበብን፡ይገዛ፡ዘንድ፡አእምሮ፡የለውም ና።
17፤ወዳጅ፡በዘመኑ፡ኹሉ፡ይወዷል፤ወንድምም፡ለመከራ፡ይወለዳል።
18፤አእምሮ፡የጐደለው፡ሰው፡ኢጋና፡ይመታል፥በባልንጀራውም፡ፊት፡ይዋሳል።
19፤ዐመፃን፡የሚወድ፡ክርክርን፡ይወዷል፤ደጁንም፡ዘለግ፡የሚያደርግ፡ውድቀትን፡ይሻል።
20፤ጠማማ፡ልብ፡ያለው፡መልካምን፡አያገኝም፥ምላሱንም፡የሚገለብጥ፡በክፉ፡ላይ፡ይወድቃል።
21፤ሰነፍን፡የሚወልድ፡ሐዘን፡ይኾንበታል፥የደንቈሮ፡ልጅም፡አባት፡ደስ፡አይለውም።
22፤ደስ፡ያላት፡ልብ፡መልካም፡መድኀኒት፡ናት፤ያዘነች፡ነፍስ፡ግን፡ዐጥንትን፡ታደርቃለች።
23፤ኃጥእ፡የፍርድን፡መንገድ፡ለማጥመም፡ከብብት፡መማለጃን፡ይወስዳል።
24፤በአስተዋይ፡ፊት፡ጥበብ፡ትኖራለች፤የሰነፍ፡ዐይን፡ግን፡በምድር፡ዳርቻ፡ነው።
25፤ሰነፍ፡ልጅ፡ለአባቱ፡ጸጸት፡ነው፥ለወለደችውም፡ምሬት፡ነው።
26፤ጻድቅን፡መቅጣት፥ጨዋ፡ሰውንም፡በጻድቅነቱ፡መምታት፡መልካም፡አይደለም።
27፤ጥቂት፡ቃልን፡የሚናገር፡ዐዋቂ፡ነው፥መንፈሱም፡ቀዝቃዛ፡የኾነ፡አስተዋይ፡ነው።
28፤ሰነፍ፡ዝም፡ቢል፡ጠቢብ፡ኾኖ፡ይቈጠራል፥ከንፈሩንም፡የሚቈልፍ፡-ባላእምሮ፡ነው፡ይባላል።
____________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡18።____________________
ምዕራፍ፡18፤
1፤መለየት፡የሚወድ፡ምኞቱን፡ይከተላል፥መልካሙንም፡ጥበብ፡ኹሉ፡ይቃወማል።
2፤ሰነፍ፡የጥበብን፡ነገር፡አይወድም፤በልቡ፡ያለውን፡ኹሉ፡መግለጥ፡ብቻ፡ይወዷል፡እንጂ።
3፤ኃጥእ፡በመጣ፡ጊዜ፡ንቀት፡ደግሞ፡ይመጣል፥ነውርም፡ከስድብ፡ጋራ።
4፤የሰው፡አፍ፡ቃል፡የጠለቀ፡ውሃ፡ነው፥የጥበብም፡ምንጭ፡ፈሳሽ፡ወንዝ፡ነው።
5፤የጻድቅ፡ፍርድ፡ይጠምም፡ዘንድ፥ለኃጥእም፡ማድላት፡መልካም፡አይደለም።
6፤የሰነፍ፡ከንፈር፡በጥል፡ውስጥ፡ትገባለች፥አፉም፡በትርን፡ትጠራለች።
7፤የሰነፍ፡አፍ፡ለራሱ፡ጥፋት፡ነው፥ከንፈሩም፡ለነፍሱ፡ወጥመድ፡ነው።
8፤የዦሮ፡ጠቢ፡ቃል፡እንደ፡ጣፋጭ፡መብል፡ነው፥ርሱም፡እስከሆድ፡ጓሮጆች፡ድረስ፡ይወርዳል።
9፤በሥራው፡ታካች፡የሚኾን፡የሀብት፡አጥፊ፡ወንድም፡ነው።
10፤የእግዚአብሔር፡ስም፡የጸና፡ግንብ፡ነው፤ጻድቅ፡ወደ፡ርሱ፡ሮጦ፡ከፍ፡ከፍ፡ይላል።
11፤ለባለጠጋ፡ሰው፡ሀብቱ፡እንደ፡ጸናች፡ከተማ፡ናት፥በዐሳቡም፡እንደ፡ረዥም፡ቅጥር።
12፤ሰው፡ሳይወድቅ፡በፊት፡ልቡ፡ከፍ፡ከፍ፡ይላል፥ትሕትናም፡ክብረትን፡ትቀድማለች።

13፤ሳይሰማ፡ነገርን፡በሚመልስ፡ስንፍናና፡ዕፍረት፡ይኾንበታል።
14፤የሰው፡ነፍስ፡ሕመሙን፡ይታገሣል፤የተቀጠቀጠን፡መንፈስ፡ግን፡ማን፡ያጠነክረዋል፤
15፤የአስተዋይ፡ልብ፡ዕውቀትን፡ያገኛል፥የጠቢባንም፡ዦሮ፡ዕውቀትን፡ትፈልጋለች።
16፤የሰው፡ስጦታ፡መንገዱን፡ታሰፋለታለች፥በታላላቆችም፡ፊት፡ታገባዋለች።
17፤ወደ፡ፍርድ፡አስቀድሞ፡የገባ፡ጻድቅ፡ይመስላል፤ባልንጀራው፡ግን፡መጥቶ፡ይመረምረዋል።
18፤ዕጣ፡ክርክርን፡ትከለክላለች፥በኀያላንም፡መካከል፡ትበይናለች።
19፤የተበደለ፡ወንድም፡እንደ፡ጸናች፡ከተማ፡ጽኑ፡ነው፤ክርክራቸውም፡እንደ፡ግንብ፡ብረት፡ነው።
20፤የሰው፡ሆድ፡ከአፉ፡ፍሬ፡ይሞላል፡ከንፈሩም፡ከሚያፈራው፡ይጠግባል።
21፤ሞትና፡ሕይወት፡በምላስ፡እጅ፡ናቸው፤የሚወዷ፟ትም፡ፍሬዋን፡ይበላሉ።
22፤ሚስት፡ያገኘ፡በረከትን፡አገኘ፥ከእግዚአብሔርም፡ሞገስን፡ይቀበላል።
23፤ድኻ፡በትሕትና፡እየለመነ፡ይናገራል፤ባለጠጋ፡ግን፡በድፍረት፡ይመልሳል።
24፤ብዙ፡ወዳጆች፡ያሉት፡ሰው፡ይጠፋል፤ነገር፡ግን፥ከወንድም፡አብልጦ፡የሚጠጋጋ፡ወዳጅ፡አለ።
__________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡19።__________________

ምዕራፍ፡19፤

1፤በከንፈሩ፡ከሚወሳልት፡ሰነፍ፡ይልቅ፡ያለነውር፡የሚኼድ፡ድኻ፡ይሻላል።
2፤ነፍስ፡ዕውቀት፡የሌለባት፡ትኾን፡ዘንድ፡መልካም፡አይደለም፤እግሩንም፡የሚያፈጥን፡ከመንገድ፡ይስታል።
3፤የሰው፡ስንፍና፡መንገዱን፡ታጣምምበታለች፤ልቡም፡በእግዚአብሔር፡ላይ፡ይቈጣል።
4፤ባለጠግነት፡ብዙ፡ወዳጆች፡ይጨምራል፤የድኻ፡ወዳጅ፡ግን፡ከርሱ፡ይርቃል።
5፤ሐሰተኛ፡ምስክር፡ሳይቀጣ፡አይቀርም፥በሐሰትም፡የሚናገር፡አያመልጥም።
6፤ብዙ፡ሰዎች፡ለጋሱን፡ያቈላምጣሉ፥ስጦታ፡ለሚሰጥም፡ዅሉ፡ወዳጅ፡ነው።
7፤ድኻን፡ሰው፡ወንድሞቹ፡ዅሉ፡ይጠሉታል፤ይልቁንም፡ወዳጆቹ፡ከርሱ፡ይርቃሉ።እነርሱንም፡በቃል፡ቢከተላቸው፡ አንዳች፡ አይረቡትም።
8፤ጥበብን፡የሚያገኝ፡ነፍሱን፡ይወዷል፥ማስተዋልንም፡የሚጠብቅ፡መልካም፡ነገርን፡ያገኛል።
9፤ሐሰተኛ፡ምስክር፡ሳይቀጣ፡አይቀርም፤በሐሰትም፡የሚናገር፡ይጠፋል።
10፤ለሰነፍ፡ቅምጥልነት፡አይገ፟ባውም፥ይልቁንም፡ባሪያ፡በአለቃዎች፡ላይ፡ይገዛ፡ዘንድ።
11፤ሰውን፡ጠቢብ፡አእምሮው፡ከቍጣ፡ያዘገየዋል፥ለበደለኛውም፡ይቅር፡ይል፡ዘንድ፡ክብር፡ይኾንለታል።
12፤እንደ፡አንበሳ፡ግሣት፡የንጉሥ፡ቍጣ፡ነው፥ሞገሱም፡በመስክ፡ላይ፡እንዳለ፡ጠል፡ነው።
13፤ሰነፍ፡ልጅ፡ለአባቱ፡ሐዘን፡ነው፥ጠበኛም፡ሚስት፡እንደማያቋርጥ፡ነጠብጣብ፡ናት።
14፤ቤትና፡ባለጠግነት፡ከአባቶች፡ዘንድ፡ይወረሳሉ፤አስተዋይ፡ሚስት፡ግን፡ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ናት።
15፤ተግባር፡መፍታት፡እንቅልፍን፡ታመጣለች፥የታካችም፡ነፍስ፡ትራባለች።
16፤ትእዛዝን፡የሚጠብቅ፡ነፍሱን፡ይጠብቃል፤መንገዱን፡ቸል፡የሚል፡ግን፡ይጠፋል።
17፤ለድኻ፡ቸርነትን፡የሚያደርግ፡ለእግዚአብሔር፡ያበድራል፥በጎነቱንም፡መልሶ፡ይከፍለዋል።
18፤ተስፋ፡ገና፡ሳለች፡ልጅኽን፡ገሥጽ፥መሞቱንም፡አትሻ።
19፤ንዴተኛ፡ሰው፡መቀጮ፡ይከፍላል፤ብታድነውም፡ደግሞ፡ትጨምራለኽ።
20፤ምክርን፡ስማ፥ተግሣጽንም፡ተቀበል፡በፍጻሜኽ፡ጠቢብ፡ትኾን፡ዘንድ።
21፤በሰው፡ልብ፡ብዙ፡ዐሳብ፡አለ፤የእግዚአብሔር፡ምክር፡ግን፡ርሱ፡ይጸናል።
22፤የሰው፡ቸርነት፡የርሱ፡ፍሬ፡ነው፤ከሐሰተኛ፡ባለጠጋም፡እውነተኛ፡ድኻ፡ይሻላል።
23፤እግዚአብሔርን፡መፍራት፡ወደ፡ሕይወት፡ይመራል፤የሚፈራውም፡ጠግቦ፡ይኖራል፥ክፉ፡ነገርም፡አያገኘውም።
24፤ታካች፡ሰው፡እጁን፡በወጭቱ፡ያጠልቃታል፥ወደ፡አፉ፡ስንኳ፡አይመልሳትም።
25፤ፌዘኛ፡ብትገርፈው፡አላዋቂ፡ብልኀተኛ፡ይኾናል፤አስተዋይን፡ሰው፡ብትገሥጸው፡ዕውቀትን፡ያገኛል።

26፤አባቱን፡የሚያስከፋ፡እናቱንም፡የሚያሳድድ፡የሚያሳፍርና፡ጐስቋላ፡ልጅ፡ነው።
27፤ልጅ፥ሆይ፥ተግሣጽን፡ከሰማኽ፡በዃላ፡ከዕውቀት፡ቃል፡መሳሳትን፡ተው።
28፤ወስላታ፡ምስክር፡በፍርድ፡ያፌዛል፥የኃጥኣንም፡አፍ፡ከፋትን፡ይውጣል።
29፤ለሚያፌዙ፡ሰዎች፡ፍርድ፡ተዘጋጅታለች፥ለሰነፎችም፡ዠርባ፡በትር።

____________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡20።____________________

ምዕራፍ፡20፤

1፤የወይን፡ጠጅ፡ፌዘኛ፡ያደርጋል፥ብርቱ፡መጠጥም፡ጠበኛ፡ያደርጋል፤በዚህም፡የሳተ፡ዅሉ፡ጠቢብ፡አይደለም።
2፤የንጉሥ፡ቍጣ፡እንደ፡አንበሳ፡ግሣት፡ነው፤የሚያስቈጣውም፡ሰው፡የራሱን፡ነፍስ፡ይበድላል።
3፤ከክርክር፡ይርቅ፡ዘንድ፡ለሰው፡ክብሩ፡ነው፤ሰነፍ፡ዅሉ፡ግን፡እንዲህ፡ባለ፡ነገር፡ይጣመራል።
4፤ታካች፡ሰው፡በብርድ፡ምክንያት፡አያርስም፤ስለዚህ፥በመከር፡ይለምናል፥ምንም፡አያገኝም።
5፤ምክር፡በሰው፡ልብ፡እንደ፡ጠሊቅ፡ውሃ፡ነው፤አእምሮ፡ያለው፡ሰው፡ግን፡ይቀዳዋል።
6፤ብዙ፡ሰዎች፡ቸርነታቸውን፡ያወራሉ፤የታመነውን፡ሰው፡ግን፡ማን፡ያገኘዋል፧
7፤ጻድቅ፡ያለነውር፡ይኼዳል፥ልጆቹም፡ከርሱ፡በዃላ፡ምስጉኖች፡ናቸው።
8፤በፍርድ፡ወንበር፡የተቀመጠ፡ንጉሥ፡ክፉውን፡ዅሉ፡በዐይኖቹ፡ይበትናል።
9፤ልቤን፡አነጻኹ፥ከኀጢአትም፡ጠራኹ፡የሚል፡ማን፡ነው፧
10፤ኹለት፡ዐይነት፡ሚዛንና፡ኹለት፡ዐይነት፡መስፈሪያ፥ኹለቱ፡በእግዚአብሔር፡ፊት፡ርኩሳን፡ናቸው።
11፤ሕፃን፡ቅንና፡ንጹሕ፡መኾኑ፡በሚያደርገው፡ሥራ፡ይታወቃል።
12፤የሚሰማ፡ዦሮንና፡የሚያይ፡ዐይንን፥ኹለቱን፡እግዚአብሔር፡ፈጠራቸው።
13፤ድኻ፡እንዳትኾን፡እንቅልፍን፡አትውደድ፤ዐይንኽን፡ክፈት፥እንጀራም፡ትጠግባለኽ።
14፤የሚገዛ፡ሰው፦ክፉ፡ነው፥ክፉ፡ነው፡ይላል፤በኼደ፡ጊዜ፡ግን፡ይመካል።
15፤ወርቅና፡ብዙ፡ቀይ፡ዕንቍ፡ይገኛል፤የዕውቀት፡ከንፈር፡ግን፡የከበረች፡ጌጥ፡ናት።
16፤ለማያውቀው፡ከተዋሰ፡ሰው፡ልብሱን፡ውሰድ፥ለእንግዳ፡የተዋሰውንም፡ርሱን፡ዐግተው።
17፤የሐሰት፡እንጀራ፡ለሰው፡የጣፈጠ፡ነው፤ከዚያ፡በዃላ፡ግን፡አፉ፡ጭንጫ፡ይሞላል።
18፤ዐሳብ፡በምክር፡ትጸናለች፥በመልካምም፡ምክር፡ሰልፍ፡አድርግ።
19፤ዘዋሪ፡ሐሜተኛ፡ምስጢርን፡ይገልጣል፤ከንፈሩን፡የሚያሞጠሙጥ፡ሰውን፡አትገናኘው።
20፤አባቱን፡ወይም፡እናቱን፡የሚሰድብ፥በድቅድቅ፡ጨለማ፡መብራቱ፡ይጠፋል።
21፤በመዠመሪያ፡ፈጥኖ፡የተከማቸ፡ርስት፡ፍጻሜው፡አይባረክም።
22፤ክፉ፡እመልሳለኹ፡አትበል፤እግዚአብሔርን፡ተማመን፥ርሱም፡ያድንኻል።
23፤ኹለት፡ዐይነት፡ሚዛን፡በእግዚአብሔር፡ዘንድ፡አስጸያፊ፡ነው፥ሐሰተኛ፡ሚዛንም፡መልካም፡አይደለም።
24፤የሰው፡አካኼዱ፡ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ነው፤እንግዲያስ፡ሰው፡መንገዱን፡እንዴት፡ያስተውላል፧
25፤ሰው፡በችኰላ፦ለእግዚአብሔር፡የተቀደሰ፡ነው፡ብሎ፡ቢሳል፥ከተሳለም፡በዃላ፡ቢጸጸት፡ወጥመድ፡ነው።
26፤ጠቢብ፡ንጉሥ፡ኃጥኣንን፡በመንሽ፡ይበትናቸዋል፥መንኰራኵሩንም፡በእነርሱ፡ላይ፡ያንኰራኵርባቸዋል።
27፤የሰው፡መንፈስ፡የእግዚአብሔር፡መብራት፡ነው፥የሆዱን፡ጕርጆች፡ዅሉ፡የሚመረምር።
28፤ቸርነትና፡እውነት፡ንጉሥን፡ይጠብቁታል፤ዙፋኑም፡በቸርነት፡ይበረታል።
29፤የጐበዛዝት፡ክብር፡ጕልበታቸው፡ናት፥የሽማግሌዎችም፡ጌጥ፡ሽበት፡ነው።
30፤የሰንበር፡ቍስል፡ክፉዎችን፡ያነጻል፤ግርፋትም፡ወደ፡ሆድ፡ጕርጆች፡ይገባል።

____________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡21።____________________

ምዕራፍ፡21፤

1፤የንጉሥ፡ልብ፡እንደ፡ውሃ፡ፈሳሾች፡በእግዚአብሔር፡እጅ፡ነው፤ወደወደደውም፡ያዘነብለዋል።
2፤የሰው፡መንገድ፡ዅሉ፡በዐይኑ፡ፊት፡የቀናች፡ትመስለዋለች፤እግዚአብሔር፡ግን፡ልብን፡ይመዝናል።

3፤እግዚአብሔር፡ከመሥዋዕት፡ይልቅ፡ጽድቅንና፡ቅን፡ነገርን፡ማድረግ፡ይወዳል።
4፤ትዕቢተኛ፡ዐይንና፡ደፋር፡ልብ፡የኃጥኣንም፡ዕርሻ፡ኀጢአት፡ነው።
5፤የትጉህ፡ዐሳብ፡ወደ፡ጥጋብ፡ያደርሳል፤ችኩል፡ሰው፡ ዅሉ፡ግን፡ለመጒደል፡ይቸኵላል።
6፤በሐሰተኛ፡ምላስ፡መዝገብ፡ማከማቸት፡የሚበኾ፡ጕም፡ነው፤ይህን፡የሚፈልጉ፡ሞትን፡ይፈልጋሉ።
7፤ቅን፡ነገርን፡ያደርጉ፡ዘንድ፡አይወዱምና፡የኃጥኣን፡ንጥቂያ፡ራሳቸውን፡ያጠፋቸዋል።
8፤የበደለኛ፡መንገድ፡የጠመመች፡ናት፤የንጹሕ፡ሥራ፡ግን፡የቀና፡ነው።
9፤ከጠበኛ፡ሴት፡ጋራ፡ባንድ፡ቤት፡ከመቀመጥ፡በውጪ፡በቤት፡ማእዘን፡ላይ፡መቀመጥ፡ይሻላል።
10፤የኃጥእ፡ነፍስ፡ክፉን፡ትመኛለች፥በፊቱም፡ባልንጀራው፡ሞገስን፡አያገኝም።
11፤ፌዘኛ፡ቅጣትን፡በተቀበለ፡ጊዜ፡አላዋቂ፡ሰው፡ጥበብን፡ያገኛል፤ጠቢብም፡ቢማር፡ዕውቀትን፡ይቀበላል።
12፤ጻድቅ፡ስለኃጥእ፡ቤት፡ያስባል፥ኃጥኣንም፡ለጥፋት፡እንደ፡ተገለበጡ።
13፤የድኻውን፡ጩኸት፡እንዳይሰማ፡ዦሮውን፡የሚደፍን፡ሰው፥ርሱ፡ራሱ፡ይጮኻል፡አይሰማለትምም።
14፤ስጦታ፡በስውር፡ቍጣን፡ታጠፋለች፥የብብትም፡ውስጥ፡ጒቦ፡ጽኑ፡ቍጣን፡ታበርዳለች።
15፤ፍርድን፡ማድረግ፡ለጻድቅ፡ደስታ፡ነው፤ኀጢአትን፡ለሚያደርጉ፡ግን፡ጥፋት፡ነው።
16፤ከማስተዋል፡መንገድ፡የሚሳሳት፡ሰው፡በሙታን፡ጉባኤ፡ያርፋል።
17፤ተድላን፡የሚወድ፡ድኻ፡ይኾናል፥የወይን፡ጠጅንና፡ዘይትንም፡የሚወድ፡ባለጠጋ፡አይኾንም።
18፤ኃጥእ፡የጻድቅ፡ቤዛ፡ነው፤በደለኛም፡የቅን፡ሰው፡ቤዛ፡ነው።
19፤ከጠበኛና፡ከቍጡ፡ሴት፡ጋራ፡ከመቀመጥ፡በምድረ፡በዳ፡መቀመጥ፡ይሻላል።
20፤የከበረ፡መዝገብና፡ዘይት፡በጠቢብ፡ሰው፡ቤት፡ይኖራል።አእምሮ፡የሌለው፡ሰው፡ግን፡ይውጠዋል።
21፤ጽድቅንና፡ምሕረትን፡የሚከተል፡ሕይወትንና፡ጽድቅን፡ክብርንም፡ያገኛል።
22፤ጠቢብ፡የኀያላንን፡ከተማ፡ይገባባታል፥የሚታመኑበትንም፡ኀይል፡ያፈርሳል።
23፤አፉንና፡ምላሱን፡የሚጠብቅ፡ነፍሱን፡ከመከራ፡ይጠብቃል።
24፤ኵሩና፡ተጓዳጅ፡ሰው፡ፌዘኛ፡ይባላል፤ርሱም፡በትዕቢት፡ቍጣ፡ያደርጋል።
25፤ታካችን፡ምኞቱ፡ትገድለዋለች፥እጆቹ፡ይሠሩ፡ዘንድ፡አይፈቅዱምና።
26፤ኃጥእ፡ቀኑን፡ ዅሉ፡ምኞትን፡ይመኛል፤ጻድቅ፡ግን፡ይሰጣል፥አይሰስትም።
27፤የኃጥኣን፡መሥዋዕት፡አስጸያፊ፡ነው፤ይልቁንም፡በክፉ፡ዐሳብ፡ሲያቀርቡት፡አስጸያፊ፡ነው።
28፤ሐሰተኛ፡ምስክር፡ይጠፋል፤የሚሰማ፡ሰው፡ግን፡ተጠንቅቆ፡ይናገራል።
29፤ኃጥእ፡ፊቱን፡ያጠነክራል፤ቅን፡ሰው፡ግን፡መንገዱን፡ያጸናል።
30፤ጥበብ፡ወይም፡ማስተዋል፡ወይም፡ምክር፡በእግዚአብሔር፡ላይ፡የለም።
31፤ፈረስ፡ለጦርነት፡ቀን፡ይዘጋጃል፤ድል፡ግን፡ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ነው።
_________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡22።________________
ምዕራፍ፡22፤
1፤መልካም፡ስም፡ከብዙ፡ባለጠግነት፡ይሻላል፥መልካምም፡ሞገስ፡ከብርና፡ከወርቅ፡ይበልጣል።
2፤ባለጠና፡ድኻ፡ተገናኙ፤እግዚአብሔር፡የዅላቸው፡ፈጣሪ፡ነው።
3፤ብልኅ፡ሰው፡ክፉን፡አይቶ፡ይሸሸጋል፤አላዋቂዎች፡ግን፡ዐልፈው፡ይጐዳሉ።
4፤ትሕትናና፡እግዚአብሔርን፡መፍራት፡ባለጠግነት፡ክብር፡ሕይወትም፡ነው።
5፤ሾኽና፡ወጥመድ፡በጠማማ፡ሰው፡መንገድ፡ናቸው፤ነፍሱን፡ግን፡የሚጠብቅ፡ከነርሱ፡ይርቃል።
6፤ልጅን፡በሚኼድበት፡መንገድ፡ምራው፥በሸመገለም፡ጊዜ፡ከርሱ፡ፈቀቅ፡አይልም።
7፤ባለጠጋ፡ድኻዎችን፡ይገዛል፥ተበዳሪም፡የአበዳሪ፡ባሪያ፡ነው።
8፤ኀጢአትን፡የሚዘራ፡መከራን፡ያጭዳል፥የቍጣውም፡በትር፡ይጠፋል።
9፤ርኅሩኅ፡የተባረከ፡ይኾናል፥ከእንጀራው፡ለድኻ፡ሰጥቷልና።

10፤ፌዘኛን፡ብታወጣ፡ክርክር፡ይወጣል፥ጠብና፡ስድብም፡ያልቃል።
11፤የልብን፡ንጽሕና፡የሚወድና፡ሞገስ፡በከንፈሩ፡ያለች፥ንጉሥ፡ወዳጁ፡ይኾናል።
12፤የእግዚአብሔር፡ዐይኖች፡ዕውቀትን፡ይጠብቃሉ፤ርሱ፡ግን፡የወስላታውን፡ቃል፡ይገለብጣል።
13፤ታካች፡ሰው፦አንበሳ፡በሜዳ፡ነው፤በመንገዱ፡ላይ፡እሞታለኹ፡ይላል።
14፤የጋለሞታ፡ሴት፡አፍ፡የጠለቀ፡ጕድጓድ፡ነው፤እግዚአብሔር፡የተቈጣው፡በርሷ፡ይወድቃል።
15፤ስንፍና፡በሕፃን፡ልብ፡ታስሯል፤የተግሣጽ፡በትር፡ግን፡ከርሱ፡ያርቃታል።
16፤ለራሱ፡ጥቅም፡ለመጨመር፡ሲል፡ድኻን፡የሚጐዳ፥ለባለጠጋም፡የሚሰጥ፥ርሱ፡ወደ፡ድኽነት፡ይወድቃል።
17፤ዦሮኽን፡አዘንብለኽ፡የጠቢባንን፡ቃላት፡ስማ፥ልብኽንም፡ወደ፡ዕውቀቴ፡አድርግ፤
18፤እነርሱን፡በውስጥኽ፡ብትጠብቅ፥በከንፈሮችኽም፡ላይ፡የተዘጋጁ፡ቢኾኑ፥የተወደደ፡ነገር፡ይኾንልኻልና።
19፤እምነትኽ፡በእግዚአብሔር፡ይኾን፡ዘንድ፡ለአንተ፡ዛሬ፥እንሆ፥አስታወቅኹኽ።
20-21፤የእውነትን፡ቃል፡ርግጥነት፡አስታውቅኽ፡ዘንድ፥ለሚጠይቅኽም፡እውነትን፡ቃል፡መመለስ፡ይቻልኽ፡ዘንድ፥ በምክርና፡
በዕውቀት፡የከበረን፡ነገር፡አልጻፍኹልኽምን፤
22፤ድኻን፡በግድ፡አትበለው፡ድኻ፡ነውና፤ችግረኛውንም፡በበር፡አትግፋው፤
23፤እግዚአብሔር፡የእነርሱን፡ፍርድ፡ይፋረድላቸዋልና፥የቀሟቸውንም፡ሰዎች፡ሕይወት፡ይቀማልና።
24፤ከቍጡ፡ሰው፡ጋራ፡ባልንጀራ፡አትኹን፥ከወፈፍተኛም፡ጋት፡አትኺድ፥
25፤መንገዱን፡እንዳትማር፡ለነፍስኽም፡ወጥመድ፡እንዳታገኝኽ።
26፤እጃቸውን፡አጋና፡እንደሚማቱ፥ለባለዕዳዎች፡እንደሚዋሱ፡አትኹን፤
27፤የምትከፍለው፡ባይኖርኽ፥ምንጣፍኽን፡ከበታችኽ፡ስለ፡ምን፡ይወስዳል፤
28፤አባቶችኽ፡የሠሩትን፡የቀድሞውን፡የድንበር፡ምልክት፡አታፍልስ።
29፤በሥራው፡የቀጠፈ፡ሰውን፡አይተኻልን፤በነገሥታት፡ፊት፡ይቆማል፤በተዋረዱም፡ሰዎች፡ፊት፡አይቆምም።
__________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡23።_________________
ምዕራፍ፡23፤
1፤ከመኰንን፡ጋራ፡ለመብላት፡በተቀመጥኽ፡ጊዜ፥በፊትኽ፡ያለውን፡በደኅና፡አስተውል፤
2፤ሰውነትኽም፡ቢሣሣ፥በጕረሮኽ፡ላይ፡ካራ፡አድርግ።
3፤ጣፋጩ፡መብል፡አይመርኽ፡የሐሰት፡እንጀራ፡ነውና።
4፤ባለጠጋ፡ለመኾን፡አትድከም፤የገዛ፡ራስኽን፡ማስተዋል፡ተው።
5፤በርሱ፡ላይ፡ዐይንኽን፡ብታዘወትርበት፡ይጠፋል፤ባለጠግነት፡ወደ፡ሰማይ፡እንደሚበሯ፡እንደ፡ንስር፡ለራሱ ፡ክንፍ፡ያበጃልና።
6፤የቀናተኛን፡ሰው፡እንጀራ፡አትብላ፥ጣፋጩ፡መብልም፡አይመርኽ፤
7፤በልቡ፡እንዳሰበ፡እንዲሁ፡ነውና፤ብላ፡ጠጣ፡ይልኻል፥ልቡ፡ግን፡ከአንተ፡ጋራ፡አይደለም።
8፤የበላኸውን፡መብል፡ትተፋዋለኽ፥ያማረውንም፡ቃልኽን፡ታጠፋዋለኽ።
9፤በሰነፍ፡ዦሮ፡አንዳች፡አትናገር፥የቃልኽን፡ጥበብ፡ያፌዝብኻልና።
10፤የቀድሞውን፡የድንበር፡ምልክት፡አታፍልስ፤ወደ፡ድኻ፡አደጎች፡ዕርሻ፡አትግባ፤
11፤ታዳጊያቸው፡ጽኑ፡ነውና፥ርሱም፡ፍርዳቸውን፡ከአንተ፡ጋራ፡ይፋረዳልና።
12፤ልብኽን፡ለተግሣጽ፡ስጥ፥ዦሮኽንም፡ወደዕውቀት፡ቃል።
13፤ሕፃንን፡ከመቅጣት፡ቸል፡አትበል፥በበትር፡ብትመታው፡አይሞትምና።
14፤በበትር፡ትመታዋለኽ፥ነፍሱንም፡ትታደጋለኽ።
15፤ልጄ፡ሆይ፥ልብኽ፡ጠቢብ፡ቢኾን፡ልቤ፡ደግሞ፡ደስ፡ይለዋል፤
16፤ከንፈሮችኽም፡በቅን፡ቢናገሩ፡ኵላሊቶቼ፡ደስ፡ይላቸዋል።
17፤ልብኽ፡በኀጢአተኞዎች፡አይቅና፤ነገር፡ግን፥ቀኑን፡ሙሉ፡እግዚአብሔርን፡በመፍራት፡ኑር፤
18፤በእውነት፡ፍጻሜ፡አለኽና፥ተስፋኽም፡አይጠፋምና።

19፤ልጄ፡ሆይ፥ስማ፡ጠቢብም፡ኹን፡ልብኽንም፡በቀናው፡መንገድ፡ምራ።
20፤የወይን፡ጠጅ፡ከሚጠጡ፡ጋራ፡አትቀመጥ፡ለሥጋም፡ከሚሣሡ፡ጋራ፤
21፤ሰካርና፡ሆዳም፡ይደኸያሉና፥የእንቅልፍም፡ብዛት፡የተቦጫጨቀ፡ጨርቅ፡ያስለብሳልና።
22፤የወለደኽን፡አባትኽን፡ስማ፥እናትኽም፡ባረጀች፡ጊዜ፡አትናቃት።
23፤እውነትን፡ግዛ፡አትሽጣትም፥ጥበብን፡ተግሣጽን፡ማስተዋልንም።
24፤የጻድቅ፡አባት፡እጅግ፡ደስ፡ይለዋል፥ጠቢብንም፡ልጅ፡የወለደ፡ሐሤትን፡ያገኛል።
25፤አባትኽና፡እናትኽ፡ደስ፡ይበላቸው፥አንተንም፡የወለደች፡ደስ፡ይበላት።
26፤ልጄ፡ሆይ፥ልብኽን፡ስጠኝ፥ዐይኖችኽም፡መንገዴን፡ይውደዱ፤
27፤ጋለሞታ፡ሴት፡የጠለቀች፡ዐዘቅት፡ናትና፥ሌላዪቱም፡ሴት፡የጠበበች፡ጕድጓድ፡ናትና።
28፤እንደ፡ሌባ፡ታደባለች፡ወስላታዎችንም፡በሰው፡ልጆች፡መካከል፡ታበዛለች።
29፤ዋይታ፡ለማን፡ነው፤ሐዘን፡ለማን፡ነው፤ጠብ፡ለማን፡ነው፤ጩኸት፡ለማን፡ነው፤ያለምክንያት፡መቍሰል፡ለማን ፡ነው፤የዐይን፡ቅላት፡ለማን፡ነው፤
30፤የወይን፡ጠጅ፡በመጠጣት፡ለሚዘገዩ፡አይደለምን፤የተደባለቀ፡የወይንን፡ጠጅ፡ይፈትኑ፡ዘንድ፡ለሚከተሉ፡አ ይደለምን፤
31፤ወደወይን፡ጠጅ፡አትመልከት፡በቀላ፡ጊዜ፥መልኩም፡በብርሌ፡ባንጸባረቀ፡ጊዜ፥እየጣፈጠም፡በገባ፡ጊዜ።
32፤በዃላ፡እንደ፡እባብ፡ይነድፋል፥እንደ፡እፉኝትም፡መርዙን፡ያፈሳል።
33፤ዐይኖችኽ፡ጋለሞታዎችን፡ያያሉ፥ልብኽም፡ጠማማ፡ነገርን፡ይናገራል።
34፤በባሕር፡ውስጥ፡እንደ፡ተኛ፡ትኾናለኽ፥በደቀልም፡ላይ፡እንደ፡ተኛ።
35፤መቱኝ፥ያውም፡አልተሰማኝም፤ጐሰሙኝ፥አላወቅኹምም፡-መቼ፡እነሣለኹ፤ደግሞ፡ጨምሬ፡እሻታለኹ፡ትላለኽ።
__________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፥ምዕራፍ፡24።__________________
ምዕራፍ፡24፤
1፤ልጄ፡ሆይ፥በክፉ፡ሰዎች፡አትቅና፥ከነርሱ፡ጋራም፡መኾንን፡አትውደድ፤
2፤ልባቸው፡ግፍን፡ታስባለችና፥ከንፈራቸውም፡ሽንገላን፡ትናገራለችና።
3፤ቤት፡በጥበብ፡ይሠራል፥በማስተዋልም፡ይጸናል።
4፤በዕውቀት፡ከከበረውና፡ካማረው፡ሀብት፡ኹሉ፡ጓዳዎች፡ይሞላሉ።
5፤ጠቢብ፡ሰው፡ብርቱ፡ነው፥ዐዋቂም፡ሰው፡ኀይሉን፡ያበዛል።
6፤በመልካም፡ሥርዐት፡ሰልፍ፡ታደርጋለኽ፤ድልም፡ብዙ፡ምክር፡ባለበት፡ዘንድ፡ነው።
7፤ጥበብ፡ለሰነፍ፡ከፍ፡ብላ፡የራቀች፡ናት፤በበርም፡አፉን፡አይከፍትም።
8፤ክፉ፡ለማድረግ፡የሚያስብ፡ተንኰለኛ፡ይባላል።
9፤የስንፍና፡ሐሳብ፡ኀጢአት፡ነው፤ሰዎች፡ፌዘኛውን፡ይጸየፉታል።
10፤በመከራ፡ቀን፡ብትላላ፡ጕልበትኽ፡ጥቂት፡ነው።
11፤ወደ፡ሞት፡የሚነዱትን፡ታደግ፤ሊታረዱ፡የተወሰኑትን፡አድን።
12፤እንሆ፥ይህን፡አላወቀውም፡ብትል፥ልቦችን፡የሚመረምር፡ርሱ፡አያስተውልምን፤ነፍስኽንም፡የሚመለከት፡ርሱ ፡አያውቅምን፤ለሰውስ፡ኹሉ፡እንደ፡ሥራው፡አይመልስለትምን፤
13፤ልጄ፡ሆይ፥መልካም፡ነውና፥ማር፡ብላ፤ወለላም፡ለጣምኽ፡ጣፋጭ፡ነው።
14፤ጥበብም፡ለነፍስኽ፡እንዲሁ፡እንደሚኾን፡ዕወቅ፤ብታገኘውም፡ፍጻሜኽ፡መልካም፡ይኾናል፥ተስፋኽም፡አይጠፋ ም።
15፤እንደ፡ኃጥእ፡በጻድቅ፡ቤት፡ላይ፡አትሸምቅ፤ማደሪያውንም፡አታውክ።
16፤ጻድቅ፡ሰባት፡ጊዜ፡ይወድቃልና፥ይነሣማል፤ኃጥኣን፡ግን፡በክፉ፡ላይ፡ይወድቃሉ።
17፤ጠላትኽ፡ቢወድቅ፡ደስ፡አይበልኽ፥በመሰናከሉም፡ልብኽ፡ሐሤት፡አያድርግ፥
18፤እግዚአብሔር፡ያንን፡አይቶ፡በዐይኑ፡ክፉ፡እንዳይኾን፥ቍጣውንም፡ከርሱ፡እንዳይመልስ።
19፤ስለ፡ኀጢአተኛዎች፡አትቈጣ፥በክፉዎችም፡አትቅና።

20፤ለኀጢአተኛ፡የፍጻሜ፡ተስፋ፡የለውምና፥የኃጥኣንም፡መብራት፡ይጠፋልና።

21፤ልጄ፡ሆይ፥እግዚአብሔርንና፡ንጉሥን፡ፍራ፥ከዐመፀኛዎችም፡ጋራ፡አትደባለቅ።

22፤መከራቸው፡ድንገት፡ይነሣልና፤ከኹለቱ፡የሚመጣውን፡ጥፋት፡ማን፡ያውቃል፧

[የሚቀጥለው፡ከግሪክ፡የተጨመረ፡ነው።]፡የነገሩትን፡የሚሰማ፡ልጅ፡ከጥፋት፡የራቀ፡ነው፤የነገሩትን፡የሚቀበልን፡ሰው፡እግዚአብሔር፡ይቀበለዋል።ከ ንጉሥ፡አንደበት፡ምንም፡ምን፡ሐሰት፡ይነገራል፡አይባልም፤ከአንደበቱም፡የሚወጣ፡ሐሰት፡የለም።የንጉሥ፡ቃል ፡ሾተል፡ናት፤ለጥፋት፡የተሰጠችውን፡ሰው፡ሰውነት፡ታጠፋዋለች፡እንጂ፡አንድ፡አካል፡ብቻ፡የምታጠፋ፡አይደለ ም።ሰይፍ፡መዓቱ፡ብትሳል፡ግን፡ከወገኑ፡ጋራ፡ሰውን፡ታጠፋለች፤ከአሞሮች፡ግልገል፡ወገን፡የማይበላ፡እስኪኾ ን፡ድረስ፡እንደ፡እሳት፡ነበልባል፡ታቃጥላለች።

23፤እነዚህ፡ደግሞ፡የጠቢባን፡ቃሎች፡ናቸው።በፍርድ፡ታደላ፡ዘንድ፡መልካም፡አይደለም።

24፤ኃጥኡን፦ጻድቅ፡ነኽ፡የሚለውን፡ወገኖች፡ይረግሙታል፡አሕዛብም፡ይጠሉታል፤

25፤የሚዘልፉት፡ግን፡ደስታ፡ይኾንላቸዋል፥በላያቸውም፡መልካም፡በረከት፡ትመጣላቸዋለች።

26፤በቀና፡ነገር፡የሚመልስ፡ከንፈርን፡ይስማል።

27፤በስተሜዳ፡ሥራኽን፡አሰናዳ፥ስለ፡አንተ፡በዕርሻ፡አዘጋጃት፤ከዚያም፡በዃላ፡ቤትኽን፡ሥራ።

28፤በባልንጀራኽ፡ላይ፡በከንቱ፡ምስክር፡አትኹን፥በከንፈርኽም፡አታባብለው።

29፤እንዳደረገብኝ፡እንዲሁ፡አደርግበታለኹ፥እንደ፡ሥራውም፡እመልስበታለኹ፡አትበል።

30፤በታካች፡ሰው፡ዕርሻ፥አእምሮ፡በጐደለውም፡ሰው፡ወይን፡ቦታ፡ዐለፍኹ።

31፤እንሆም፥ኹሉ፡ሾኽ፡ሞልቶበታል፥ፊቱንም፡ሳማ፡ሸፍኖታል፥የድንጋዩም፡ቅጥር፡ፈርሷል።

32፤ተመለከትኹና፡ዐሰብኹ፤አየኹትና፡ተግሣጽን፡ተቀበልኹ።

33፤ጥቂት፡ትተኛለኽ፥ጥቂትም፡ታንቀላፋለኽ፥ትተኛም፡ዘንድ፡ጥቂት፡እጅኽን፡ታጥፋለኽ፤

34፤እንግዲህ፡ድኽነትኽ፡እንደ፡ወንበዴ፥ችጋርኽም፡ሰይፍ፡እንደ፡ታጠቀ፡ሰው፡ይመጣብኻል፡፡

# መጽሐፈ፡ተግሣጽ።

(ከሉሳ.1.20020507)

____________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፡(መጽሐፈ፡ተግሣጽ)፥ምዕራፍ፡25።____________________

ምዕራፍ፡25፤(1)፡

1፤እነዚህም፡ደግሞ፡የይሁዳ፡ንጉሥ፡የሕዝቅያስ፡ሰዎች፡የቀዷቸው፡የሰሎሞን፡ምሳሌዎች፡ናቸው።
2፤የእግዚአብሔር፡ክብር፡ነገርን፡መሰወር፡ነው፤የነገሥታት፡ክብር፡ግን፡ነገርን፡መመርመር፡ነው።
3፤እንደሰማይ፡ከፍታ፡እንደምድርም፡ጥልቀት፡የነገሥታት፡ልብ፡አይመረመርም።
4፤ከብር፡ዝገትን፡አስወግድ፥ፈጽሞም፡ይጠራል።
5፤ከንጉሥ፡ፊት፡ኃጥኣንን፡አርቅ፥ዙፋኑም፡በጽድቅ፡ትጸናለች።
6፤በንጉሥ፡ፊት፡አትመካ፥በታላልቆችም፡ስፍራ፡አትቁም፤
7፤ዐይኖችኽ፡ባዩት፡በመኰንን፡ፊት፡ከምትዋረድ።ወደዚህ፡ከፍ፡በል፡ብትባል፡ይሻልኻልና።
8፤ባልንጀራኽ፡ባሳፈረኽ፡ጊዜ፡ኋላ፡እንዳትጸጸት፡ለክርክር፡ፈጥነኽ፡አትውጣ፤
9፤ክርክርኽን፡ከባልንጀራኽ፡ጋራ፡ተከራከር፤የሌላ፡ሰው፡ምስጢር፡ግን፡አትግለጥ፥
10፤የሚሰማ፡እንዳይነቅፍኽ፥አንተንም፡ከማነወር፡ዝም፡እንዳይል።
11፤የወርቅ፡እንኮይ፡በብር፡ጻሕል፡ላይ፤የጊዜው፡ቃል፡እንዲሁ፡ነው።
12፤የምትሰማን፡ዦሮ፡የሚዘልፍ፡ጠቢብ፡ሰው፡እንደ፡ወርቅ፡ጕትቻ፡እንደሚያንጸባርቅም፡ዕንቍ፡እንዲሁ፡ነው።
13፤በመከር፡ወራት፡የውርጭ፡ጠል፡ደስ፡እንደሚያሠኝ፥እንዲሁ፡የታመነ፡መልእክተኛ፡ለላኩት፡ነው፤የጌታዎቹን ፡ነፍስ፡ያሳርፋልና።
14፤ስለ፡ስጦታው፡በሐሰት፡የሚመካ፡ሰው፡ዝናብ፡እንደማይከተለው፡ደመና፡ነፋስም፡ነው።
15፤በትዕግሥት፡አለቃ፡ይለዝባል፥የገራም፡ምላስ፡ዐጥንትን፡ይሰብራል።
16፤አጥብቀኽ፡እንዳትጠግብ፡እንዳትተፋውም፡ማር፡ባገኘኽ፡ጊዜ፡የሚበቃኽን፡ብላ።
17፤እንዳይሰለችኽ፡እንዳይጠላኽም፥እግርኽን፡ወደባልንጀራኽ፡ቤት፡አታዘውትር።
18፤በባልንጀራው፡በሐሰት፡የሚመሰክር፡እንደ፡መዶሻና፡እንደ፡ሰይፍ፡እንደ፡ተሳለም፡ፍላጻ፡ነው።
19፤ወስላታውን፡ሰው፡በመከራ፡ጊዜ፡መተማመን፡እንደ፡ተሰበረ፡ጥርስና፡እንደ፡ሰለለ፡እግር፡ነው።
20፤ለሚያዝን፡ልብ፡ዝማሬ፡የሚዘምር፥ለብርድ፡ቀን፡መጐናጸፊያውን፡እንደሚያስወግድ፡በቍስልም፡ላይ፡እንደ፡ መጻጻ፡እንዲሁ፡ነው።
21፤ጠላትኽ፡ቢራብ፡እንጀራ፡አብላው፥ቢጠማም፡ውሃ፡አጠጣው፤
22፤ፍም፡በራሱ፡ላይ፡ትሰበስባለኽና፥እግዚአብሔርም፡ዋጋኽን፡ይመልስልኻልና።
23፤የሰሜን፡ነፋስ፡ወጀብ፡ያመጣል፤ሐሜተኛ፡ምላስም፡የሰውን፡ፊት፡ያስቈጣል።
24፤ከጠበኛ፡ሴት፡ጋራ፡ባንድ፡ቤት፡ከመቀመጥ፡በሰገነት፡ማእዘን፡መቀመጥ፡ይሻላል።
25፤የቀዘቀዘ፡ውሃ፡ለተጠማች፡ነፍስ፡ደስ፡እንደሚያሠኝ፥ከሩቅ፡አገር፡የመጣ፡መልካም፡ምሥራች፡እንዲሁ፡ነው ።
26፤በኃጥእ፡ፊት፡የሚወድቅ፡ጻድቅ፡እንደደፈረሰ፡ፈሳሽና፡እንደ፡ረከሰ፡ምንጭ፡ነው።
27፤ብዙ፡ማር፡መብላት፡መልካም፡አይደለም፤እንዲሁም፡የራስን፡ክብር፡መፈላለግ፡አያስከብርም።
28፤ቅጥር፡እንደሌላት፡እንደ፡ፈረሰች፡ከተማ፥መንፈሱን፡የማይከለክል፡ሰው፡እንዲሁ፡ነው።

____________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፡(መጽሐፈ፡ተግሣጽ)፥ምዕራፍ፡26።____________________

ምዕራፍ፡26፤(2)፡

1፤በረዶ፡በበጋ፡ዝናብም፡በመከር፡እንዳይገ̈ባ፥እንዲሁ፡ለሰነፍ፡ክብር፡አይገ̈ባውም።
2፤እንደሚተላለፍ፡ድንቢጥ፡ወዲያና፡ወዲህም፡እንደሚበ̈ር፡ጨረባ፥እንዲሁ፡ከንቱ፡ርግማን፡በማንም፡ላይ፡አይ ደርስም።
3፤ዐለንጋ፡ለፈረስ፥ልጓም፡ለአህያ፥በትርም፡ለሰነፍ፡ዠርባ፡ነው።
4፤አንተ፡ደግሞ፡ርሱን፡እንዳትመስል፡ለሰነፍ፡እንደ፡ስንፍናው፡አትመልስለት።
5፤ለራሱ፡ጠቢብ፡የኾነ፡እንዳይመስለው፡ለሰነፍ፡እንደ፡ስንፍናው፡መልስለት።
6፤በሰነፍ፡መልእክተኛ፡እጅ፡ነገርን፡የሚልክ፡እግሮቹን፡ይቈርጣል፡ግፍንም፡ይጠጣል።
7፤እንደሚንጠለጠሉ፡የዐንካሳ፡እግሮች፥እንዲሁም፡ምሳሌ፡በሰነፎች፡አፍ፡ነው።

8፤ለሰነፍ፡ክብርን፡የሚሰጥ፡ድንጋይን፡በወንጭፍ፡እንደሚያስር፡ነው።
9፤ሾኽ፡በሰካር፡እጅ፡እንደሚሰካ፥እንዲሁ፡ምሳሌ፡በሰነፎች፡አፍ፡ነው።
10፤ዋና፡ሠራተኛ፡ዅሉን፡ነገር፡ይሠራል፤ሰነፍን፡የሚቀጥር፡ግን፡መንገድ፡ዐላፊውን፡እንደሚቀጥር፡ነው።
11፤ወደ፡ትፋቱ፡እንደሚመለስ፡ውሻ፡ስንፍናውን፡የሚደግም፡ሰው፡እንዲሁ፡ነው።
12፤ለራሱ፡ጠቢብ፡የኾነ፡የሚመስለውን፡ሰው፡አየኸውን፤ከርሱ፡ይልቅ፡ለሰነፍ፡ተስፋ፡አለው።
13፤ታካች፡ሰው፦አንበሳ፡በመንገድ፡አለ፤አንበሳ፡በጐዳና፡አለ፡ይላል።
14፤ሳንቃ፡በማጠፊያው፡ላይ፡እንደሚዞር፥እንዲሁ፡ታካች፡ሰው፡በዐልጋው፡ላይ፡ይመላለሳል።
15፤ታካች፡ሰው፡እጁን፡ወደ፡ወጭት፡ያጠልቃል፤ወደ፡አፉም፡ይመልሳት፡ዘንድ፡ለርሱ፡ድካም፡ነው።
16፤ታካች፡ሰው፡በጥበብ፡ከሚመልሱ፡ከሰባት፡ሰዎች፡ይልቅ፡ለራሱ፡ጠቢብ፡የኾነ፡ይመስለዋል።
17፤ዐልፎ፡በሌላው፡ጥል፡የሚደባለቅ፡ውሻን፡በዥራቱ፡እንደሚይዝ፡ነው።
18፤ትንታግንና፡ፍላጻን፡ሞትንም፡እንደሚወረውር፡እንደ፡እብድ፡ሰው፥
19፤ባልንጀራውን፡የሚያታልል፦በጨዋታ፡አደረግኹት፡የሚል፡ሰውም፡እንዲሁ፡ነው።
20፤ዕንጨት፡ባለቀ፡ጊዜ፡እሳት፡ይጠፋል፤ጕሮ፡ጠቢ፡በሌለበትም፡ዘንድ፡ጠብ፡ጸጥ፡ይላል።
21፤ከሰል፡ፍምን፡ዕንጨትም፡እሳትን፡እንዲያበዛ፥እንዲሁ፡ቍጡ፡ሰው፡ጠብን፡ያበዛል።
22፤የጕሮ፡ጠቢ፡ቃል፡እንደ፡ጣፋጭ፡መብል፡ነው፥ርሱም፡እስከሆድ፡ጕርጆች፡ድረስ፡ይወርዳል።
23፤ከፋት፡በልቡ፡ሳለ፡ፍቅርን፡የሚናገር፡ከንፈር፡በብር፡ዝገት፡እንደ፡ተለበጠ፡የሸክላ፡ዕቃ፡ነው።
24፤ጠላት፡በከንፈሩ፡ተስፋ፡ይሰጣል፥በልቡ፡ግን፡ተንኰልን፡ያኖራል።
25፤በልቡ፡ሰባት፡ርኵሰት፡አለበትና፡በቃሉ፡አሳምሮ፡ቢናገርኽ፡አትመነው።
26፤ጠላትነቱን፡በተንኰል፡የሚሸሽግ፥ክፋቱ፡በጉባኤ፡መካከል፡ይገለጣል።
27፤ጕድጓድን፡የሚምስ፡ይወድቅበታል፤ድንጋይንም፡የሚያንከባልል፡ይገለበጥበታል።
28፤ሐሰተኛ፡ምላስ፡ያቈሰላቸውን፡ሰዎች፡ይጠላል፤ልዝብ፡አፍም፡ጥፋትን፡ያመጣል።
____________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፡(መጽሐፈ፡ተግሣጽ)፥ምዕራፍ፡27።____________________
ምዕራፍ፡27፤(3)፡
1፤ቀን፡የሚያመጣውን፡ምን፡እንደ፡ኾነ፡አታውቅምና፡ነገ፡በሚኾነው፡አትመካ።
2፤ሌላ፡ያመስግንኽ፡እንጂ፡አፍኽ፡አይደለም፤ባዕድ፡ሰው፡እንጂ፡ከንፈርኽ፡አይደለም።
3፤ድንጋይ፡ከባድ፡ነው፥አሸዋም፡ሸክሙ፡ጽኑ፡ነው፤ከኹለቱ፡ግን፡የሰነፍ፡ቍጣ፡ይከብዳል።
4፤ቍጣ፡ምሕረት፡የሌለው፡ነው፥መዓትም፡እንደ፡ጐርፍ፡ነው፤በቅንአት፡ፊት፡ግን፡ማን፡ይቆማል፧
5፤የተገለጠ፡ዘለፋ፡ከተሰወረ፡ፍቅር፡ይሻላል።
6፤የወዳጅ፡ማቍሰል፡የታመነ፡ነው፤የጠላት፡መሳም፡ግን፡የበዛ፡ነው።
7፤የጠገበች፡ነፍስ፡የማር፡ወለላ፡ትረግጣለች፤ለተራበች፡ነፍስ፡ግን፡የመረረ፡ነገር፡ዅሉ፡ይጣፍጣታል።
8፤ስፍራውን፡የሚተው፡ሰው፥ቤቱን፡ትቶ፡እንደሚበርር፡ወፍ፡ነው።
9፤ሽቱና፡ዕጣን፡ልብን፡ደስ፡ያሠኛሉ፤እንዲሁ፡ነፍስ፡በወዳጁ፡ምክር፡ደስ፡ይላታል።
10፤ወዳጅኽንና፡የአባትኽን፡ወዳጅ፡አትተው፤በመከራኽም፡ቀን፡ወደወንድምኽ፡ቤት፡አትግባ፤የቀረበ፡ወዳጅ፡ከ ራቀ፡ወንድም፡ይሻላል።
11፤ልጄ፡ሆይ፥ጠቢብ፡ኹን፥ልቤንም፡ደስ፡አሠኘው፥ለሚሰድበኝ፡መልስ፡መስጠት፡ይቻለኝ፡ዘንድ።
12፤ብልኅ፡ሰው፡ክፉን፡አይቶ፡ይሸሸጋል፤አላዋቂዎች፡ግን፡ዐልፈው፡ይጐዳሉ።
13፤ለማያውቀው፡ከተዋሰ፡ሰው፡ልብሱን፡ውሰድ፥ለእንግዳ፡የተዋሰውንም፡ርሱን፡ዐግተው።
14፤ባልንጀራውን፡በታላቅ፡ቃል፡ማለዳ፡የሚባርክ፡ሰው፡እንደሚራገም፡ያኸል፡ነው።
15፤በዝናብ፡ቀን፡የሚያንጠባጥብ፡ቤትና፡ጠበኛ፡ሴት፡አንድ፡ናቸው፤
16፤ርሷንም፡መከልከል፡ነፋስን፡መከልከልና፡ዘይትን፡በቀኝ፡እጅ፡መጨበጥ፡ነው።
17፤ብረት፡ብረትን፡ይስለዋል፥ሰውም፡ባልንጀራውን፡ይስላል።
18፤በለሱን፡የጠበቀ፡ፍሬዋን፡ይበላል፥ጌታውንም፡የሚጠብቅ፡ይከብራል።
19፤ፊት፡በውሃ፡ላይ፡ለፊት፡እንደሚታይ፥እንዲሁ፡የሰው፡ልብ፡ለሰው፡ይታያል።
20፤ሲኦልና፡ጥፋት፡እንዳይጠግቡ፥እንዲሁ፡የሰው፡ዐይን፡አይጠግብም።
21፤ብር፡በከውር፡ወርቅም፡በማቅለጫ፡ይፈተናል፤ሰውም፡በሚያመሰግኑት፡ሰዎች፡አፍ፡ይፈተናል።
22፤ሰነፍን፡በሙቀጫ፡ውስጥ፡ከእኽል፡ጋራ፡በዘነዘና፡ብትወቅጠው፥ስንፍናው፡ከርሱ፡አይርቅም።
23፤የበጎችኽን፡መልክ፡አስተውለኽ፡ዕወቅ፥በከብቶችኽም፡ላይ፡ልብኽን፡አኑር፤

24፤ባለጠግነት፡ለዘለዓለም፡አይኖርምና፥ዘውድም፡ለትውልድ፡ኹሉ፡አይጸናምና።
25፤ደረቅ፡ሣር፡በታጨደ፡ጊዜ፥ዐዲስ፡ለምለም፡በታየ፡ጊዜ፥ከተራራውም፡ቡቃያ፡በተሰበሰበ፡ጊዜ፥
26፤በጎች፡ለልብስኽ፡ፍየሎችም፡የዕርሻ፡ዋጋ፡ይኾናሉ።
27፤ለሲሳይኽ፡ለቤተ፡ሰቦችኽም፡ሲሳይ፡ለገረዶችኽም፡ምግብ፡የፍየል፡ወተት፡ይበቃል።
_________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፡(መጽሐፈ፡ተግሣጽ)፥ምዕራፍ፡28።________________
ምዕራፍ፡28፤(4)፡
1፤ኃጥእ፡ማንም፡ሳያሳድደው፡ይሸሻል፤ጻድቅ፡ግን፡እንደ፡አንበሳ፡ያለፍርሀት፡ይኖራል።
2፤ስለአገሪቱ፡ዐመፀኝነት፡አለቃዎቿ፡ብዙ፡ኾኑ፤በአስተዋይና፡በዐዋቂ፡ሰው፡ግን፡ዘመኗ፡ይረዝማል።
3፤ድኻዎችን፡የሚያስጨንቅ፡ምስኪን፡ሰው፡እኽልን፡እንደሚያጠፋ፡እንደ፡ዶፍ፡ዝናብ፡ነው።
4፤ሕግን፡የሚተዉ፡ሰዎች፡ኃጥኣንን፡ያመሰግናሉ፤ሕግ፡ጠባቂዎች፡ግን፡ይጠሏቸዋል።
5፤ክፉዎች፡ሰዎች፡ፍርድን፡አያስተውሉም፤እግዚአብሔርን፡የሚሹ፡ግን፡ኹሉን፡ያስተውላሉ።
6፤በጠማማ፡መንገድ፡ከሚኼድ፡ባለጠጋ፡ያለነውር፡የሚኼድ፡ድኻ፡ይሻላል።
7፤ሕግን፡የሚጠብቅ፡አስተዋይ፡ልጅ፡ነው፤ምናምንቴዎችን፡የሚከተል፡ግን፡አባቱን፡ያሳፍራል።
8፤በዐራጣ፡ብዛትና፡በቅሚያ፡ሀብቱን፡የሚያበዛ፡ለድኻ፡ለሚራራ፡ያከማችለታል።
9፤ሕግን፡ከመስማት፡ዠሮውን፡የሚመልስ፡ጸሎቱ፡አስጸያፊ፡ናት።
10፤ቅኖችን፡በክፉ፡መንገድ፡የሚያስት፥ርሱ፡ወደ፡ጒድጓዱ፡ይወድቃል፤ፍጹማን፡ግን፡መልካም፡ነገርን፡ይወርሳ ሉ።
11፤ባለጠጋ፡ሰው፡ለራሱ፡ጠቢብ፡የኾነ፡ይመስለዋል፤አስተዋይ፡ድኻ፡ግን፡ይመረምረዋል።
12፤ጻድቃን፡ድል፡ባደረጉ፡ጊዜ፡ብዙ፡ክብር፡አለ፤ኃጥኣን፡ከፍ፡ከፍ፡ባሉ፡ጊዜ፡ግን፡ሰው፡ይሸሸጋል።
13፤ኀጢአቱን፡የሚሰውር፡አይለማም፤የሚናዘዝባትና፡የሚተዋት፡ግን፡ምሕረትን፡ያገኛል።
14፤ኹልጊዜ፡የሚፈራ፡ሰው፡ምስጉን፡ነው፤ልቡን፡የሚያጸና፡ግን፡በክፉ፡ላይ፡ይወድቃል።
15፤በድኻ፡ሕዝብ፡ላይ፡የሚገዛ፡ክፉ፡መኰንን፡እንደሚያገሣ፡አንበሳና፡እንደ፡ተራበ፡ድብ፡ነው።
16፤አእምሮ፡የጐደለው፡መኰንን፡ትልቅ፡ግፈኛ፡ነው፤ግፍን፡የሚጠላ፡ግን፡ብዙ፡ዘመን፡ይኖራል።
17፤የሰው፡ደም፡ያለበት፡ሰው፡እንደ፡ጒድጓድ፡ይሸሻል፥ማንም፡አያስጠጋውም።
18፤በቅንነት፡የሚኼድ፡ይድናል፤በጠማምነት፡የሚኼድ፡ግን፡ወዲያው፡ይወድቃል።
19፤ምድሩን፡የሚያርስ፡እንጀራ፡ይጠግባል፤ምናምንቴዎችን፡የሚከተል፡ግን፡ድኽነት፡ይሞላበታል።
20፤የታመነ፡ሰው፡እጅግ፡ይባረካል፤ባለጠጋ፡ለመኾን፡የሚቸኵል፡ግን፡ሳይቀጣ፡አይቀርም።
21፤ማድላት፥በቍራሽ፡እንጀራም፡መበደል፡መልካም፡አይደለም።
22፤ምቀኛ፡ሰው፡ባለጠጋ፡ለመኾን፡ይቸኵላል፥ችጋርም፡እንደሚመጣበት፡አያውቅም።
23፤ምላሱን፡ከሚያጣፍጥ፡ይልቅ፡ሰውን፡የሚገሥጽ፡በኋላ፡ሞገስ፡ያገኛል።
24፤ከአባቱና፡ከእናቱ፡የሚሰርቅ፡-ኀጢአትን፡አልሠራኹም፡የሚልም፡የአጥፊ፡ባልንጀራ፡ነው።
25፤የሚጐመዥ፡ሰው፡ክርክርን፡ያነሣሣል፤በእግዚአብሔር፡የሚታመን፡ግን፡ይጠግባል።
26፤በገዛ፡ልቡ፡የሚታመን፡ሰው፡ሰነፍ፡ነው፤በጥበብ፡የሚኼድ፡ግን፡ይድናል።
27፤ለድኻ፡የሚሰጥ፡አያጣም፤ዐይኖቹን፡የሚጨፍን፡ግን፡እጅግ፡ይረገማል።
28፤ኃጥኣን፡በተነሡ፡ጊዜ፡ሰዎች፡ይሸሸጋሉ፤እነርሱ፡በጠፉ፡ጊዜ፡ግን፡ጻድቃን፡ይበዛሉ።
_________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፡(መጽሐፈ፡ተግሣጽ)፥ምዕራፍ፡29።________________
ምዕራፍ፡29፤(5)፡
1፤ብዙ፡ጊዜ፡ተዘልፎ፡ዐንገቱን፡ያደነደነ፡ድንገት፡ይሰበራል፥ፈውስም፡የለውም።
2፤ጻድቃን፡በበዙ፡ጊዜ፡ሕዝብ፡ደስ፡ይለዋል፤ኃጥኣን፡በሠለጠኑ፡ጊዜ፡ግን፡ሕዝብ፡ያለቅሳል።
3፤ጥበብን፡የወደደ፡ሰው፡አባቱን፡ደስ፡ያሠኛል፤ጋለሞታዎችን፡የሚከተል፡ግን፡ሀብቱን፡ያጠፋል።
4፤ንጉሥ፡በፍርድ፡አገሩን፡ያጸናል፤መማለጃ፡የሚወድ፡ግን፡ያፈርሰዋል።
5፤ወዳጁን፡በለዘበ፡ቃል፡የሚናገር፡ሰው፡ለእግሩ፡መርበብን፡ይዘረጋል።
6፤በክፉ፡ሰው፡ዐመፃ፡ወጥመድ፡ይገኛል፤ጻድቅ፡ግን፡ደስ፡ይለዋል፥እልልም፡ይላል።
7፤ጻድቅ፡የድኻዎችን፡ፍርድ፡ይመለከታል፤ኃጥእ፡ግን፡ዕውቀትን፡አያስተውልም።
8፤ፌዘኞዎች፡ከተማቸውን፡ያቃጥላሉ፤ጠቢባን፡ግን፡ቍጣን፡ይመልሳሉ።
9፤ጠቢብ፡ከሰነፍ፡ጋራ፡ቢጣላ፥ሰነፍ፡ወይም፡ይቈጣል፡ወይም፡ይሥቃል፥ዕረፍትም፡የለም።
10፤ደምን፡ለማፍሰስ፡የሚሹ፡ሰዎች፡ፍጹሙን፡ሰው፡ይጠላሉ፥ደግሞም፡የቅኑን፡ሰው፡ነፍስ፡ይሻሉ።

11፧ሰነፍ፡ሰው፡ቍጣውን፡ኹሉ፡ያወጣል፤ጠቢብ፡ግን፡በውስጡ፡ያስቀረዋል።
12፧መኰንን፡ሐሰተኛ፡ነገርን፡ቢያደምጥ፥ከርሱ፡በታች፡ያሉት፡ኹሉ፡ዐመፅኞች፡ይኾናሉ።
13፧ድኻና፡ግፈኛ፡ተገናኙ፤እግዚአብሔር፡የኹለቱንም፡ዐይን፡ያበራል።
14፧ለድኻ፡በእውነት፡የሚፈርድ፡ንጉሥ፥ዙፋኑ፡ለዘለዓለም፡ይጸናል።
15፧በትርና፡ተግሣጽ፡ጥበብን፡ይሰጣሉ፤ያልተቀጣ፡ብላቴና፡ግን፡እናቱን፡ያሳፍራል።
16፧ኃጥኣን፡ሲበዙ፡ኀጢአት፡ትበዛለች፤ጻድቃን፡ግን፡ውደቀታቸውን፡ያያሉ።
17፧ልጅኽን፡ቅጣ፡ዕረፍትንም፡ይሰጥኻል፤ለነፍስኽም፡ተድላን፡ይሰጣታል።
18፧ራእይ፡ባይኖር፡ሕዝብ፡መረን፡ይኾናል፤ሕግን፡የሚጠብቅ፡ግን፡የተመሰገነ፡ነው።
19፧ባሪያ፡በቃል፡አይገሠጽም፤ቢያስተውል፡እንኳ፡አይመልስምና።
20፧በቃሉ፡የሚቸኵለውን፡ሰው፡ብታይ፥ከርሱ፡ይልቅ፡ለሰነፍ፡ተስፋ፡አለው።
21፧ባሪያውን፡ከሕፃንነቱ፡ዠምሮ፡በማቀማጠል፡የሚያሳድግ፡የኋላ፡ኋላ፡እንደ፡ጌታ፡ያደርገዋል።
22፧ቍጡ፡ሰው፡ክርክርን፡ያነሣሣል።ወፈፍተኛ፡ሰውም፡ኀጢአትን፡ያበዛል።
23፧ሰውን፡ትዕቢቱ፡ያዋርደዋል፤መንፈሱን፡የሚያዋርድ፡ግን፡ክብርን፡ይቀበላል።
24፧ከሌባ፡ጋራ፡የሚካፈል፡ነፍሱን፡ይጠላል፤መርገምን፡ይሰማል፥ነገር፡ግን፥ምንም፡አይገልጥም።
25፧ሰውን፡መፍራት፡ወጥመድ፡ያመጣል፤በእግዚአብሔር፡የሚታመን፡ግን፡ርሱ፡ይጠበቃል።
26፧ብዙ፡ሰዎች፡የሹምን፡ፊት፡ይሻሉ፤የሰው፡ፍርድ፡ግን፡ከእግዚአብሔር፡ዘንድ፡ነው።
27፧ኀጢአተኛ፡በጻድቃን፡ዘንድ፡አስጸያፊ፡ነው፤በቀና፡መንገድ፡የሚኼደውም፡በኃጥኣን፡ዘንድ፡አስጸያፊ፡ነው ።
________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፡(መጽሐፈ፡ተግሣጽ)፥ምዕራፍ፡30።________________
ምዕራፍ፡30፤(6)፡
1፧የማሣ፡አገር፡ሰው፡የያቄ፡ልጅ፡የአጉር፡ቃል፡ሰውየው፡ለኢቲኤልና፡ለኡካል፡እንደዚህ፡ይናገራል።
2፧እኔ፡በእውነት፡ከሰው፡ኹሉ፡ይልቅ፡ደንቈሮ፡ነኝ፥የሰውም፡ማስተዋል፡የለብኝም።
3፧ጥበብንም፡አልተማርኹም፥ቅዱሱንም፡አላወቅኹትም።
4፧ወደ፡ሰማይ፡የወጣ፡የወረደስ፡ማን፡ነው፤ነፋስንስ፡በእጁ፡የጨበጠ፡ማን፡ነው፤ውሃንስ፡በልብሱ፡የቋጠረ፡ማ ን፡ነው፤የምድርን፡ዳርቻ፡ኹሉ፡ያጸና፡ማ
ነው፤ይህን፡ታውቅ፡እንደ፡ኾንኽ፥ስሙ፡ማን፡የልጁስ፡ስም፡ማን፡ ነው፤
5፧የእግዚአብሔር፡ቃል፡ኹሉ፡ተፈትናለች፤ርሱ፡ለሚታመኑት፡ጋሻ፡ነው።
6፧እንዳይዘልፍኽ፥ሐሰተኛም፡እንዳትኾን፡በቃሉ፡አንዳች፡አትጨምር።
7፧ኹለትን፡ነገር፡ከአንተ፡እሻለኹ፥ሳልሞትም፡አትከልክለኝ፤
8፧ከንቱነትንና፡ሐሰተኛነትን፡ከእኔ፡አርቃቸው፤ድኽነትንና፡ባለጠግነትን፡አትስጠኝ፤ነገር፡ግን፥የሚያስፈል ገኝን፡እንጀራ፡ስጠኝ፥
9፧እንዳልጠግብ፡እንዳልክድኽም፦እግዚአብሔርስ፡ማን፡ነው፤እንዳልል፤ድኻም፡እንዳልኾን፡እንዳልሰርቅም፥በአ ምላኬም፡ስም፡በሐሰት፡እንዳልምል
10፧እንዳይሰድብኽ፡በደለኛም፡እንዳትኾን፡ባሪያን፡በጌታው፡ፊት፡አትማ።
11፧አባቱን፡የሚረግም፥እናቱንም፡የማይባርክ፡ትውልድ፡አለ።
12፧ለራሱ፡ንጹሕ፡የኾነ፡የሚመስለው፡ከርኵሰቱ፡ያልጠራ፡ትውልድ፡አለ።
13፧ከፍ፡ከፍ፡ያሉ፡ዐይኖች፡ያሉት፥ሽፋሽፍቶቹም፡ወደ፡ላይ፡የሚያዩ፡ትውልድ፡አለ።
14፧ድኻዎችን፡ከምድር፡ላይ፡ችግረኛዎችንም፡ከሰው፡መካከል፡ያጠፋና፡ይጨርስ፡ዘንድ፡ጥርሶቹ፡ሰይፍ፡መንጋጋ ቹም፡ካራ፡የኾኑ፡ትውልድ፡አለ።
15፧ዐልቅት፦ስጠን፡ስጠን፡የሚሉ፡ኹለት፡ሴቶች፡ልጆች፡አሉት።ሦስቱ፡የማይጠግቡ፥አራቱም፦በቃን፡የማይሉ፡ና ቸው፤
16፧እነርሱም፡ሲኦልና፡የማትወልድ፡ማሕፀን፡ውሃ፡የማትጠግብ፡ምድርና፦በቃኝ፡የማትል፡እሳት፡ናቸው።
17፧በአባቷ፡የምታላግጥን፡የእናቷንም፡ትእዛዝ፡የምትንቅን፡ዐይን፡የሸለቆ፡ቍራዎች፡ይጐጠጒጧታል፥አሞራዎች ም፡ይበሏታል።
18፧ሦስት፡ነገር፡ይገርመኛል፥አራተኛውንም፡ከቶ፡አላስተውለውም።
19፧እነርሱም፡የንስር፡መንገድ፡በሰማይ፥የእባብ፡መንገድ፡በድንጋይ፡ላይ፥የመርከብ፡መንገድ፡በባሕር፡ላይ፥ የሰውም፡መንገድ፡ከቈንዦ፡ጋራ፡ናቸው።
20፧እንዲሁ፡በልታ፡አፏን፡የምታብስ፦አንዳች፡ክፉ፡ነገር፡አላደረግኹም፡የምትልም፡የአመንዝራ፡ሴት፡መንገድ ፡ናት።
21፧በሦስት፡ነገር፡ምድር፡ትናወጣለች፥አራተኛውንም፡ትሸከም፡ዘንድ፡አይቻላትም።
22፧ባሪያ፡በነገሠ፡ጊዜ፡ሰነፍም፡እንጀራ፡በጠገበ፡ጊዜ፥
23፧የተጠላች፡ሴት፡ባል፡ባገኘች፡ጊዜ፥ሴት፡ባሪያም፡እመቤቷን፡በወረሰች፡ጊዜ።
24፧በምድር፡ላይ፡አራት፡ጥቃቅን፡ፍጥረቶች፡አሉ፤እነርሱ፡ግን፡እጅግ፡ጠቢባን፡ናቸው፤
25፧ገብረ፡ጕንዳን፡ኀይል፡የሌላቸው፡ሕዝቦች፡ናቸው፥ነገር፡ግን፥በበጋ፡መኗቸውን፡ይሰበስባሉ።
26፧ሽኮኮዎች፡ያልበረቱ፡ሕዝቦች፡ናቸው፥ቤታቸውን፡ግን፡በቋጥኝ፡ድንጋይ፡ውስጥ፡ያደርጋሉ።

27፤አንበጣዎች፡ንጉሥ፡የላቸውም፥ዅላቸው፡ግን፡በመልካም፡ሥርዐት፡ይኼዳሉ።
28፤እንሽላሊት፡በእጅ፡ይያዛል፥በነገሥታት፡ግቢ፡ግን፡ይኖራል።
29፤መልካም፡አረማመድን፡የሚራመዱ፡ሦስት፡ፍጥረቶች፡አሉ፥አራተኛውም፡መልካም፡አካኼድን፡ይኼዳል፤
30፤የአንበሳ፡ደቦል፡ከእንስሳ፡ዅሉ፡የሚበረታ፥የማይመለስ፥እንስሳንም፡የማይፈራ፤
31፤በእንስቶች፡መካከል፡በድፍረት፡የሚራመድ፡አውራ፡ዶሮ፤መንጋን፡የምመራ፡አውራ፡ፍየል፤በሕዝብ፡ፊት፡በግ ልጥ፡የሚናገር፡ንጉሥ።
32፤ከፍ፡ከፍ፡ስትል፡ስንፍናን፡ያደረግኽ፡እንደ፡ኾነ፥ክፉም፡ያሰብኽ፡እንደ፡ኾነ፥እጅኽን፡በአፍኽ፡ላይ፡ጫ ን።
33፤ወተት፡መግፋት፡ቅቤን፡ያወጣል፥አፍንጫንም፡መጭመቅ፡ደምን፡ያወጣ፤እንዲሁም፡ቍጣን፡መጐተት፡ጠብን፡ያወ ጣል።
__________________መጽሐፈ፡ምሳሌ፡(መጽሐፈ፡ተግሣጽ)፥ምዕራፍ፡31።__________________
ምዕራፍ፡31፤(6)፡
1፤እናቱ፡ርሱን፡ያስተማረችበት፡የማሣ፡ንጉሥ፡የልሙኤል፡ቃል።
2፤ልጄ፡ሆይ፥ምንድር፡ነው፧የሆዴ፡ልጅ፡ሆይ፥ምንድር፡ነው፧የስእለቴ፡ልጅ፡ሆይ፥ምንድር፡ነው፧
3፤ጕልበትኽን፡ለሴቶች፡አትስጥ፥መንገድኽንም፡ነገሥታትን፡ለሚያጠፉ።
4፤ለነገሥታት፡አይገ̈ባም፥ልሙኤል፡ሆይ፥ነገሥታት፡የወይን፡ጠጅ፡ይጠጡ፡ዘንድ፡አይገ̈ባም።መሳፍንትም፦ ብርቱ፡መጠጥ፡ወዴት፡ነው፧ይሉ፡ዘንድ፤
5፤እንዳይጠጡና፡ሕግን፡እንዳይረሱ፥የድኻ፡ልጆችንም፡ፍርድ፡እንዳያጐድሉ።
6፤ለጥፋት፡ለቀረበው፡ሰው፡ብርቱ፡መጠጥ፡ስጡት፥ነፍሱ፡ለመረረውም፡የወይን፡ጠጅ፡ስጡት፤
7፤ይጠጣ፡ድኽነቱንም፡ይርሳ፥ጕስቍልናውንም፡ከእንግዲህ፡ወዲህ፡አያስብ።
8፤አፍኽን፡ስለ፡ዲዳው፡ክፈት፥ተስፋ፡ስለሌላቸውም፡ዅሉ፡ተፋረድ።
9፤አፍኽን፡ክፈት፥በእውነትም፡ፍረድ፤ለድኻና፡ለምስኪን፡ፍረድ።
10፤ልባም፡ሴትን፡ማን፡ሊያገኛት፡ይችላል፧ዋጋዋ፡ከቀይ፡ዕንቍ፡እጅግ፡ይበልጣል።
11፤የባሏ፡ልብ፡ይታመንባታል።ምርኮም፡አይጐድልበትም።
12፤ዕድሜዋን፡ሙሉ፡መልካም፡ታደርግለታለች፥ክፉም፡አታደርግም።
13፤የበግ፡ጠጕርና፡የተልባ፡እግር፡ትፈልጋለች፥በእጆቿም፡ደስ፡ብሏት፡ትሠራለች።
14፤ርሷ፡እንደ፡ነጋዴ፡መርከብ፡ናት፤ከሩቅ፡አገር፡ምግቧን፡ትሰበስባለች።
15፤ገና፡ሌሊት፡ሳለ፡ትነሣለች፡ለቤቷም፡ሰዎች፡ምግባቸውን፥ለገረዶቿም፡ተግባራቸውን፡ትሰጣለች።
16፤ዕርሻንም፡ተመልክታ፡ትገዛለች፤ከእጇም፡ፍሬ፡ወይን፡ትተክላለች።
17፤ወገቧን፡በኀይል፡ትታጠቃለች፥ክንዷንም፡ታበረታለች።
18፤ንግዷ፡መልካም፡እንደ፡ኾነ፡ትመለከታለች፤መብራቷ፡በሌሊት፡አይጠፋም።
19፤እጇን፡ወደ፡አመልማሎ፡ትዘረጋለች፥ጣቶቿም፡እንዝርትን፡ይይዛሉ።
20፤እጇን፡ወደ፡ድኻ፡ትዘረጋለች፥ወደ፡ችግረኛም፡እጇን፡ትሰዳለች።
21፤ለቤቷ፡ሰዎች፡ከበረዶ፡ብርድ፡የተነሣ፡አትፈራም፥የቤቷ፡ሰዎች፡ዅሉ፡ዕጥፍ፡ድርብ፡የለበሱ፡ናቸውና።
22፤ለራሷም፡ግብረ፡መርፌ፡ስጋጃ፡ትሠራለች፡ጥሩ፡በፍታና፡ቀይ፡ግምጃ፡ትለብሳለች።
23፤ባሏ፡በአገር፡ሽማግሌዎች፡መካከል፡በሸንጎ፡በተቀመጠ፡ጊዜ፡በበር፡የታወቀ፡ይኾናል።
24፤የበፍታ፡ቀሚስ፡እየሠራች፡ትሸጣለች፥ለነጋዴም፡ድግ፡ትሸጣለች።
25፤ብርታትና፡ክበሬታ፡ልብሷ፡ነው፤በኋላም፡ዘመን፡ላይ፡ትሥቃለች።
26፤አፏን፡በጥበብ፡ትከፍታለች፤የርኅራኄም፡ሕግ፡በምላሷ፡አለ።
27፤የቤቷንም፡ሰዎች፡አካኼድ፡በደኅና፡ትመለከታለች፥የሀኬትንም፡እንጀራ፡አትበላም።
28፤ልጆቿ፡ይነሣሉ፥ምስጋናዋንም፡ይናገራሉ፤ባሏ፡ደግሞ፡እንዲህ፡ብሎ፡ያመሰግናታል።
29፤መልካም፡ያደረጉ፡ብዙ፡ሴቶች፡አሉ፥አንቺ፡ግን፡ከዅሉ፡ትበልጫለሽ።
30፤ውበት፡ሐሰት፡ነው፥ደም፡ግባትም፡ከንቱ፡ነው፤እግዚአብሔርን፡የምትፈራ፡ሴት፡ግን፡ርሷ፡ትመሰገናለች።
31፤ከእጇ፡ፍሬ፡ስጧት፥ሥራዎቿም፡በሸንጎ፡ያመስግኗት፡፡

# መጽሐፈ፡መክብብ።

(ክለሳ.1.20020507)

___________________መጽሐፈ፡መክብብ፥ምዕራፍ፡1።_________________

ምዕራፍ፡1።

1፤በኢየሩሳሌም፡የነገሠ፡የሰባኪው፡የዳዊት፡ልጅ፡ቃል።

2፤ሰባኪው፦ከንቱ፥ከንቱ፥የከንቱ፡ከንቱ፥ዅሉ፡ከንቱ፡ነው፡ይላል።

3፤ከፀሓይ፡በታች፡በሚደክምበት፡ድካም፡ዅሉ፡የሰው፡ትርፉ፡ምንድር፡ነው፤

4፤ትውልድ፡ይኼዳል፥ትውልድም፡ይመጣል፤ምድር፡ግን፡ለዘለዓለም፡ነው።

5፤ፀሓይ፡ትወጣለች፥ፀሓይም፡ትገባለች፥ወደምትወጣበትም፡ስፍራ፡ትቸኵላለች።

6፤ነፋስ፡ወደ፡ደቡብ፡ይኼዳል፥ወደ፡ሰሜንም፡ይዞራል፤ዘወትር፡በዙረቱ፡ይዞራል፥ነፋስም፡በዙረቱ፡ደግሞ፡ይመ ለሳል።

7፤ፈሳሾች፡ዅሉ፡ወደ፡ባሕር፡ይኼዳሉ፥ባሕሩ፡ግን፡አይሞላም፤ፈሳሾች፡ወደሚኼዱበት፡ስፍራ፡እንደ፡ገና፡ወደዚ ያ፡ይመለሳሉ።

8፤ነገር፡ዅሉ፡ያደክማል፡ሰው፡ይናገረው፡ዘንድ፡አይችልም፤ዐይን፡ከማየት፡አይጠግብም፥ዦሮም፡ከመስማት፡አይ ሞላም።

9፤የኾነው፡ነገር፡ርሱ፡የሚኾን፡ነው፥የተደረገውም፡ነገር፡ርሱ፡የሚደረግ፡ነው፤ከፀሓይም፡በታች፡ዐዲስ፡ነገ ር፡የለም።

10፤ማንም፦እንሆ፥ይህ፡ነገር፡ዐዲስ፡ነው፡ይል፡ዘንድ፡ይችላልን፧ርሱ፡ከእኛ፡በፊት፡በነበሩት፡ዘመናት፡ተደ ርጓል።

11፤ለፊተኛዎቹ፡ነገሮች፡መታሰቢያ፡የላቸውም፤ከዃለኛዎቹም፡ነገሮች፡ከነርሱ፡በዃላ፡በሚነሡት፡ሰዎች፡ዘንድ ፡መታሰቢያ፡አይገኝላቸውም።

12፤እኔ፡ሰባኪው፡በእስራኤል፡ላይ፡በኢየሩሳሌም፡ንጉሥ፡ነበርኹ።

13፤ከሰማይም፡በታች፡የተደረገውን፡ዅሉ፡በጥበብ፡እፈልግና፡እመረምር፡ዘንድ፡ልቤን፡አተጋኹ፤እግዚአብሔር፡ ይደክሙባት፡ዘንድ፡ይህችን፡ለሰው፡
ልጆች፡የሰጠ፡ክፉ፡ጥረት፡ናት።

14፤ከፀሓይ፡በታች፡የተሠራውን፡ሥራ፡ዅሉ፡አየኹ፤እንሆም፥ዅሉ፡ከንቱ፡ነው፥ነፋስንም፡እንደ፡መከተል፡ነው።

15፤ጠማማ፡ይቀና፡ዘንድ፡አይችልም፤ጐደሎም፡ይቈጠር፡ዘንድ፡አይችልም።

16፤እኔ፡በልቤ፦እንሆ፥ከእኔ፡አስቀድመው፡በኢየሩሳሌም፡ላይ፡ከነበሩት፡ዅሉ፡ይልቅ፡ጥበብን፡አብዝቼ፡ጨመር ኹ፤ልቤም፡ብዙ፡ጥበብንና፡ዕውቀት
ተመለከተ፡ብዬ፡ተናገርኹ።

17፤ጥበብንና፡እብደትን፡ሞኝነትንም፡ዐውቅ፡ዘንድ፡ልቤን፡ሰጠኹ፤ይህም፡ደግሞ፡ነፋስን፡እንደ፡መከተል፡እን ደ፡ኾነ፡አስተዋልኹ።

18፤በጥበብ፡መብዛት፡ትካዜ፡ይበዛልና፤ዕውቀትንም፡የሚጨምር፡ሐዘንን፡ይጨምራልና።

___________________መጽሐፈ፡መክብብ፥ምዕራፍ፡2።_________________

ምዕራፍ፡2።

1፤እኔ፡በልቤ፦ና፥በደስታም፡እፈትንኻለኹ፥መልካምንም፡ቅመስ፡አልኹ፤ይህም፡ደግሞ፥እንሆ፥ከንቱ፡ነበረ።

2፤ሣቅን፦እብድ፡ነኽ፤ደስታንም፦ምን፡ታደርጋለኽ፧አልኹት።

3፤የሰው፡ልጆች፡በሕይወታቸው፡ዘመን፡ዅሉ፡ከፀሓይ፡በታች፡ሊሠሩት፡መልካም፡ነገር፡ምን፡እንደ፡ኾነ፡እስካይ ፡ድረስ፥ልቤ፡በጥበብ፡እየመራኝ፥
ሰውነቴን፡በወይን፡ጠጅ፡ደስ፡ለማሠኘት፥ስንፍናንም፡ለመያዝ፡በልቤ፡መረመ ርኹ።

4፤ትልቅ፡ሥራን፡ሠራኹ፥ቤቶችንም፡አደረግኹ፥ወይንም፡ተከልኹ፤

5፤አትክልትንና፡ገነትን፡አደረግኹ፥ልዩ፡ልዩ፡ፍሬ፡ያለባቸውንም፡ዛፎች፡ተከልኹባቸው፤

6፤በዱር፡የተተከሉትን፡ዛፎች፡አጠጣበት፡ዘንድ፡የውሃ፡ማጠራቀሚያ፡አደረግኹ።

7፤ወንዶችንና፡ሴቶችን፡ባሪያዎች፡ገዛኹ፥የቤት፡ውልድ፡ባሪያዎችም፡ነበሩኝ፤ከእኔ፡አስቀድመው፡በኢየሩሳሌም ፡ከነበሩት፡ዅሉ፡ይልቅ፡ብዙ፡ከብቶች
መንጋዎች፡ነበሩኝ።

8፤ብርንና፡ወርቅን፡የከበረውንም፡የነገሥታትና፡የአውራጃዎችን፡መዝገብ፡ሰበሰብኹ፤አዝማሪዎችንና፡አረኾዎች ን፡የሰዎች፡ልጆችንም፡ተድላ፡እጅግ፡
የበዙ፡ሴቶችንም፡አከማቸኹ።

9፤ታላቅም፡ኾንኹ፥ከእኔም፡አስቀድመው፡በኢየሩሳሌም፡ከነበሩት፡ዅሉ፡ይልቅ፡ከበርኹ፤ደግሞም፡ጥበቤ፡ከእኔ፡ ጋራ፡ጸንታ፡ቀረች።

10፤ዐይኖቼንም፡ከፈለጉት፡ዅሉ፡አልከለከልዃቸውም፤ልቤም፡በድካሜ፡ዅሉ፡ደስ፡ይለው፡ነበርና፥ልቤን፡ከደስታ ፡ዅሉ፡አላራቅኹትም፥ከድካሜም
ዅሉ፡ይህ፡ዕድል፡ፈንታዬ፡ኾነ።

11፤እጄ፡የሠራቻትን፡ሥራዬን፡ዅሉ፡የደከምኹበትንም፡ድካሜን፡ዅሉ፡ተመለከትኹ፤እንሆ፥ዅሉ፡ከንቱ፡ነፋስንም ፡እንደ፡መከተል፡ነበር፥ከፀሓይ፡
በታችም፡ትርፍ፡አልነበረም።

12፤እኔም፡ጥበብን፡እብደትንና፡ስንፍናን፡አይ፡ዘንድ፡ተመለከትኹ፤በፊት፡ከተደረገው፡በቀር፥ከንጉሥ፡በኋላ ፡የሚመጣው፡ሰው፡ምን፡ያደርጋል፧
13፤እኔም፡ብርሃን፡ከጨለማ፡እንደሚበልጥ፡እንዲሁ፡ጥበብ፡ከስንፍና፡እንዲበልጥ፡አየኹ።
14፤የጠቢብ፡ዐይኖች፡በራሱ፡ላይ፡ናቸው፥ሰነፍ፡ግን፡በጨለማ፡ይኼዳል፤ደግሞ፡ለኹለቱ፡መጨረሻቸው፡አንድ፡እ ንደ፡ኾነ፡አስተዋልኹ።
15፤እኔም፡በልቤ፦ለሰነፍ፡የሚደርሰው፡ለኔም፡ይደርሳል፤ለምን፡እጅግ፡ጠቢብ፡ኾንኹ፤አልኹ።የዚያን፡ጊዜም፡ በልቤ፦ይህ፡ደግሞ፡ከንቱ፡ነው፡አልኹ
16፤በሚመጣው፡ዘመን፡ነገር፡ኹሉ፡የተረሳ፡ይኾናልና፥ለዘለዓለም፡የሚኾን፡የጠቢብና፡የሰነፍ፡መታሰቢያ፡አይ ገኝም።አዬ፡ጕድ! ጠቢብ፡ከሰነፍ፡ጋራ
እንዴት፡ይሞታል!
17፤ከፀሓይም፡በታች፡የተሠራው፡ሥራ፡ኹሉ፡ከብዶብኛልና፥ሕይወትን፡ጠላኹ፤ኹሉም፡ከንቱ፡ነፋስንም፡እንደ፡መ ከተል፡ነው።
18፤ከእኔ፡በኋላ፡ለሚመጣው፡ሰው፡እተወዋለኹና፡ከፀሓይ፡በታች፡የደከምኹበትን፡ኹሉ፡ጠላኹት።
19፤ጠቢብ፡ወይም፡ሰነፍ፡እንዲኾን፡የሚያውቅ፡ሰው፡ማን፡ነው፧ከፀሓይ፡በታች፡በደከምኹበትና፡ጠቢብ፡በኾንኹ በት፡በድካሜ፡ኹሉ፡ላይ፡ጌታ፡
ይኾንበታል፤ይህም፡ደግሞ፡ከንቱ፡ነው።
20፤እኔም፡ተመልሼ፡ልቤን፡ከፀሓይ፡በታች፡በደከምኹበት፡ድካም፡ኹሉ፡ተስፋ፡አስቈረጥኹት።
21፤ሰው፡በጥበብና፡በዕውቀት፡በብልኀትም፡ከደከመ፡በኋላ፡ለሌላ፡ላልደከመበት፡ሰው፡ያወርሰዋልና፤ይህም፡ደ ግሞ፡ከንቱ፡ትልቅም፡መከራ፡ነው።
22፤ከፀሓይ፡በታች፡በደከመበት፡ድካም፡ኹሉና፡በልቡ፡ዐሳብ፡የሰው፡ጥቅም፡ምንድር፡ነው፧
23፤ዘመኑ፡ኹሉ፡ሐዘን፥ጥረትም፡ትካዜ፡ነው፤ልቡም፡በሌሊት፡አይተኛም፤ይህም፡ደግሞ፡ከንቱ፡ነው።
24፤ለሰው፡ከሚበላና፡ከሚጠጣ፡በድካሙም፡ደስ፡ከሚለው፡በቀር፡የሚሻለው፡ነገር፡የለም፤ይህም፡ደግሞ፡ከእግዚ አብሔር፡እጅ፡እንደ፡ተሰጠ፡አየኹ።
25፤ያለርሱ፡ፈቃድ፡የበላ፡ደስ፡ብሎትም፡ተድላን፡የቀመሰ፡ማን፡ነው፧
26፤ርሱም፡ደስ፡ለሚያሠኘው፡ሰው፡ጥበብንና፡ዕውቀትን፡ደስታንም፡ይሰጠዋል፤ለኀጢአተኛ፡ግን፡እግዚአብሔርን ፡ደስ፡ለሚያሠኘው፡ሰው፡ይሰጥ፡
ዘንድ፡እንዲሰበስብና፡እንዲያከማች፡ጥረትን፡ይሰጠዋል።ይህም፡ደግሞ፡ከንቱ ፡ነፋስንም፡እንደ፡መከተል፡ነው።
__________________________መጽሐፈ፡መክብብ፥ምዕራፍ፡3።__________________________
ምዕራፍ፡3።
1፤ለኹሉ፡ዘመን፡አለው፥ከሰማይ፡በታችም፡ለኾነ፡ነገር፡ኹሉ፡ጊዜ፡አለው።
2፤ለመወለድ፡ጊዜ፡አለው፥ለመሞትም፡ጊዜ፡አለው፤ለመትከል፡ጊዜ፡አለው፥የተተከለውንም፡ለመንቀል፡ጊዜ፡አለው ፤
3፤ለመግደል፡ጊዜ፡አለው፥ለመፈወስም፡ጊዜ፡አለው፤ለማፍረስ፡ጊዜ፡አለው፥ለመሥራትም፡ጊዜ፡አለው፤
4፤ለማልቀስ፡ጊዜ፡አለው፥ለመሣቅም፡ጊዜ፡አለው፤ዋይ፡ለማለት፡ጊዜ፡አለው፥ለመዝፈንም፡ጊዜ፡አለው፤
5፤ድንጋይን፡ለመጣል፡ጊዜ፡አለው፥ድንጋይንም፡ለመሰብሰብ፡ጊዜ፡አለው፤ለመተቃቀፍ፡ጊዜ፡አለው፥ከመተቃቀፍም ፡ለመራቅ፡ጊዜ፡አለው፤
6፤ለመፈለግ፡ጊዜ፡አለው፥ለማጥፋትም፡ጊዜ፡አለው፤ለመጠበቅ፡ጊዜ፡አለው፥ለመጣልም፡ጊዜ፡አለው፤
7፤ለመቅደድ፡ጊዜ፡አለው፥ለመስፋትም፡ጊዜ፡አለው፤ዝም፡ለማለት፡ጊዜ፡አለው፥ለመናገርም፡ጊዜ፡አለው፤
8፤ለመውደድ፡ጊዜ፡አለው፥ለመጥላትም፡ጊዜ፡አለው፤ለጦርነት፡ጊዜ፡አለው፥ለሰላምም፡ጊዜ፡አለው።
9፤ለሠራተኛ፡የድካሙ፡ትርፍ፡ምንድር፡ነው፧
10፤እግዚአብሔር፡ለሰው፡ልጆች፡ይደክሙበት፡ዘንድ፡የሰጣቸውን፡ጥረት፡አይቻለኹ።
11፤ነገርን፡ኹሉ፡በጊዜው፡ውብ፡አድርጎ፡ሠራው፤እግዚአብሔርም፡ከጥንት፡ዠምሮ፡እስከ፡ፍጻሜ፡ድረስ፡የሠራው ን፡ሥራ፡ሰው፡መርምሮ፡እንዳያገኝ፡
ዘለዓለምነትን፡በልቡ፡ሰጠው።
12፤ሰው፡ደስ፡ከሚለውና፡በሕይወቱ፡ሳለ፡መልካምን፡ነገር፡ከሚያደርግ፡በቀር፡መልካም፡ነገር፡እንደሌለ፡ዐወ ቅኹ።
13፤ደግሞም፡ሰው፡ኹሉ፡ይበላና፡ይጠጣ፡ዘንድ፡በድካሙም፡ኹሉ፡ደስ፡ይለው፡ዘንድ፡የእግዚአብሔር፡ስጦታ፡ነው ።
14፤እግዚአብሔር፡ያደረገው፡ኹሉ፡ለዘለዓለም፡እንዲኖር፡ዐወቅኹ፤ሊጨመርበት፡ወይም፡ከርሱ፡ሊጐድል፡አይቻል ም፤እግዚአብሔርም፡በፊቱ፡ይፈሩ፡
ዘንድ፡አደረገ።
15፤አኹን፡ያለው፡በፊት፡ነበረ፥የሚኾነውም፡በፊት፡ኾኖ፡ነበር፤እግዚአብሔርም፡ያለፈውን፡መልሶ፡ይሻዋል።
16፤ደግሞም፡ከፀሓይ፡በታች፡በፍርድ፡ስፍራ፡ኀጢአት፥በጽድቅም፡ስፍራ፡ኀጢአት፡እንዳለ፡አየኹ።
17፤እኔም፡በልቤ፦በዚያ፡ለነገር፡ኹሉና፡ለሥራ፡ኹሉ፡ጊዜ፡አለውና፡በጻድቅና፡በኀጢአተኛ፡ላይ፡እግዚአብሔር ፡ይፈርዳል፡አልኹ።
18፤እኔ፡በልቤ፡ስለሰው፡ልጆች፦እንደ፡እንስሳ፡መኾናቸውን፡እንዲያዩ፡እግዚአብሔር፡ይፈትናቸዋል፡አልኹ።
19፤የሰው፡ልጆችና፡የእንስሳ፡ዕድል፡ፈንታ፡አንድ፡ነው፤ድርሻቸውም፡ትክክል፡ነው፤አንዱ፡እንደሚሞት፡ሌላው ም፡እንዲሁ፡ይሞታል፤የኹሉም፡
እስትንፋስ፡አንድ፡ነው፤ኹሉም፡ከንቱ፡ነውና፥ሰው፡ከእንስሳ፡ብልጫ፡የለውም።
20፤ኹሉ፡ወደ፡አንድ፡ቦታ፡ይኼዳል፤ኹሉ፡ከዐፈር፡ነው፥ኹሉም፡ወደ፡ዐፈር፡ይመለሳል።
21፤የሰው፡ልጆች፡ነፍስ፡ወደ፡ላይ፡እንደምትወጣ፥የእንስሳም፡ነፍስ፡ወደ፡ታች፡ወደ፡ምድር፡እንደምትወርድ፡ የሚያውቅ፡ማን፡ነው፧
22፤ያም፡ዕድል፡ፈንታው፡ነውና፥ሰው፡በሥራው፡ደስ፡ከሚለው፡በቀር፡ሌላ፡መልካም፡ነገር፡እንደሌለው፡አየኹ፤ ከርሱ፡በኋላስ፡የሚኾነውን፡ያይ፡ዘን
የሚያመጣው፡ማን፡ነው፧

______________ መጽሐፈ፡መክብብ፥ምዕራፍ፡4። ______________

ምዕራፍ፡4።

1፤እኔም፡ተመለስኹ፥ከፀሓይ፡በታችም፡የሚደረገውን፡ግፍ፡ኹሉ፡አየኹ፤እንሆም፥የተገፉት፡ሰዎች፡እንባ፡ነበረ ፤የሚያጽናናቸውም፡አልነበረም፤በሚገፏቸውም፡እጅ፡ኀይል፡ነበረ፥እነርሱን፡ግን፡የሚያጽናናቸው፡አልነበረም ።

2፤እኔም፡እስከ፡ዛሬ፡በሕይወት፡ካሉት፡ይልቅ፡በቀድሞ፡ዘመን፡የሞቱትን፡አመሰገንኹ፤

3፤ከነዚህም፡ከኹለቱ፡ይልቅ፡ገና፡ያልተወለደው፡ከፀሓይም፡በታች፡የሚደረገውን፡ግፍ፡ያላየው፡ይሻላል።

4፤ደግሞም፡የሰውን፡ድካምና፡የብልኀት፡ሥራውን፡ኹሉ፡ተመለከትኹ፥በባልንጀራውም፡ዘንድ፡ቅንአት፡እንዲያስነ ሣ፡አየኹ፤ይህም፡ደግሞ፡ከንቱ፡ነፋስንም፡እንደ፡መከተል፡ነው።

5፤ሰነፍ፡እጆቹን፡ኰርትሞ፡ይቀመጣል፤የገዛ፡ሥጋውንም፡ይበላል።

6፤በድካምና፡ነፋስን፡በመከተል፡ከኹለት፡እጅ፡ሙሉ፡ይልቅ፡አንድ፡እጅ፡ሙሉ፡በዕረፍት፡ይሻላል።

7፤እኔም፡ተመለስኹ፥ከፀሓይ፡በታችም፡ከንቱን፡ነገር፡አየኹ።

8፤አንድ፡ሰው፡ብቻውን፡አለ፥ኹለተኛም፡የለውም፡ልጅም፡ኾነ፡ወንድም፡የለውም፤ለድካሙ፡ግን፡መጨረሻ፡የለውም ፥ዐይኖቹም፡ከባለጠግነት፡አይጠግቡም፡-ለማን፡እደክማለኹ፥ሰውነቴንስ፡መልካሙን፡ነገር፡ለምን፡እነፍጋታለኹ ፤ይላል።ይህም፡ደግሞ፡ከንቱ፡ነገር፣ክፉም፡ጥረት፡ነው።

9፤ድካማቸው፡መልካም፡ዋጋ፡አለውና፥አንድ፡ብቻ፡ከመኾን፡ኹለት፡መኾን፡ይሻላል።

10፤ቢወድቁ፡አንዱ፡ኹለተኛውን፡ያነሣዋልና፤አንዱ፡ብቻውን፡ኾኖ፡በወደቀ፡ጊዜ፡ግን፡የሚያነሣው፡ኹለተኛ፡የ ለውምና፡ወዮለት።

11፤ኹለቱም፡በአንድነት፡ቢተኙ፥ይሞቃቸዋል፤አንድ፡ብቻውን፡ግን፡እንዴት፡ይሞቀዋል፧

12፤አንዱም፡አንዱን፡ቢያሸንፍ፥ኹለቱ፡በፊቱ፡ይቆማሉ፤በሦስትም፡የተገመደ፡ገመድ፡ፈጥኖ፡አይበጠስም።

13፤ድኻና፡ጠቢብ፡ብላቴና፥ተግሣጽን፡መቀበል፡ከእንግዲህ፡ወዲህ፡ከማያውቅ፡ከሰነፍ፡ሽማግሌ፡ንጉሥ፡ይሻላል ።

14፤ምንም፡በመንግሥቱ፡አገር፡ደግሞ፡ችግረኛ፡ኾኖ፡ቢወለድ፥ከግዞቱ፡ቤት፡ወደ፡መንግሥት፡ወጥቷልና።

15፤ከፀሓይ፡በታች፡የሚኼዱትን፡ሕያዋን፡ኹሉ፡በርሱ፡ፋንታ፡ከሚነሣው፡ከሌላው፡ጐበዝ፡ጋራ፡ኾነው፡አየኹ።

16፤ከርሱ፡በፊት፡የተገዙለት፡ሕዝብ፡ኹሉ፡አይቈጠሩም፤በኋላ፡የሚመጡት፡ግን፡በርሱ፡ደስ፡አይላቸውም።ይህም ፡ደግሞ፡ከንቱ፡ነፋስንም፡እንደ፡መከተል፡ነው።

______________ መጽሐፈ፡መክብብ፥ምዕራፍ፡5። ______________

ምዕራፍ፡5።

1፤ወደእግዚአብሔር፡ቤት፡በገባኽ፡ጊዜ፡እግርኽን፡ጠብቅ፤ለመስማት፡መቅረብ፡ከሰነፎች፡መሥዋዕት፡ይበልጣልና ፤እነርሱም፡ክፉ፡እንዲያደርጉ፡አያውቁምና።

2፤እግዚአብሔር፡በሰማይ፥አንተም፡በምድር፡ነኽና፥በአፍኽ፡አትፍጠን፥በእግዚአብሔርም፡ፊት፡ቃልን፡ይናገር፡ ዘንድ፡ልብኽ፡አይቸኵል፤ስለዚህም፡ቃልኽ፡ጥቂት፡ትኹን።

3፤ሕልም፡በሥራ፡ብዛት፡ይታያል፤እንዲሁም፡የሰነፍ፡ድምፅ፡በቃሉ፡ብዛት፡ይሰማል።

4፤ሰነፎች፡ደስ፡አያሠኙትምና፡ለእግዚአብሔር፡ስእለት፡በተሳልኽ፡ጊዜ፡ትፈጽመው፡ዘንድ፡አትዘግይ፤የተሳልኸ ውን፡ፈጽመው።

5፤ተስለኽ፡የማትፈጽም፡ብትኾን፡ባትሳል፡ይሻላል።

6፤ሥጋኽን፡በኀጢአት፡እንዳያስተው፡ለአፍኽ፡ሐራነት፡አትስጥ፥በመልአክም፡ፊት፡-ስሕተት፡ነበረ፡አትበል፤እግ ዚአብሔር፡በቃልኽ፡ይቈጣ፡ዘንድ፡የእጅኽንም፡ሥራ፡ያጠፋ፡ዘንድ፡ስለ፡ምን፡ትሻለኽ፧

7፤ብዙ፡ሕልም፡ባለበት፡ዘንድ፥እንዲሁም፡ደግሞ፡ብዙ፡ቃል፡ባለበት፡ስፍራ፡በዚያ፡ብዙ፡ከንቱ፡ነገር፡አለ፤አ ንተ፡ግን፡እግዚአብሔርን፡ፍራ።

8፤ከፍ፡ካለው፡በላይ፡ከፍ፡ያለ፡ይመለከታልና፥ከነርሱም፡በላይ፡ደግሞ፡ሌላዎች፡ከፍ፡ይላሉና፡በአገሩ፡ድኻዎ ች፡ሲገፉ፥ፍርድና፡ጽድቅም፡ሲነጠቅ፡ባየ ጊዜ፡በዚህ፡ነገር፡አታድንቅ።

9፤በጠቅላላው፡ግን፡የአገሩ፡ጥቅም፡ዕርሻን፡የሚወድ፡ንጉሥ፡ቢኖር፡ነው።

10፤ብርን፡የሚወድ፡ሰው፡ብርን፡አይጠግብም፤ባለጠግነትንም፡የሚወድ፡ትርፉን፡አይጠግብም፤ይህም፡ደግሞ፡ ከንቱ፡ነው።

11፤ሀብት፡ሲበዛ፡የሚበሉት፡ይበዛሉ፤ሀብቱን፡በዐይኑ፡ብቻ፡ከማየት፡በቀር፡ለባለቤቱ፡ምን፡ይጠቅመዋል፧

12፤እጅግ፡ወይም፡ጥቂት፡ቢበላ፡የሠራተኛ፡እንቅልፍ፡ጣፋጭ፡ነው፥የባለጠጋ፡ጥጋብ፡ግን፡እንቅልፍን፡ይከለክ ለዋል።

13፤ከፀሓይ፡በታች፡የሚያሳዝን፡ክፉ፡ነገር፡አየኹ፤ለመከራው፡በባለቤቱ፡ዘንድ፡የተቈጠበች፡ባለጠግነት፡ናት ።

14፤ያችም፡ባለጠግነት፡በክፉ፡ነገር፡ትጠፋለች፤ልጅንም፡ቢወልድ፡በእጁ፡ምንም፡የለውም።

15፤ከእናቱ፡ሆድ፡ዕራቍቱን፡እንደ፡ወጣ፡እንዲሁ፡እንደመጣው፡ይመለሳል፤ከጥረቱም፡በእጁ፡ሊወስድ፡የሚችለው ን፡ምንም፡አያገኝም።

16፤ይህም፡ደግሞ፡የሚያሳዝን፡ክፉ፡ነገር፡ነው፤እንደ፡መጣ፡እንዲሁ፡ይኼዳል፤ድካሙም፡ለነፋስ፡ከኾነ፡ጥቅሙ ፡ምንድር፡ነው፧

17፤ዘመኑን፡ኹሉ፡በጨለማ፡በሐዘን፡በብስጭት፡በደዌና፡በቍጣ፡ነው።

18፤እንሆ፥እኔ፡ያየኹት፡መልካምና፡የተዋበ፡ነገር፡ሰው፡እግዚአብሔር፡በሰጠው፡በሕይወቱ፡ዘመን፡ኹሉ፡ይበላ ና፡ይጠጣ፡ዘንድ፥ከፀሓይ፡በታችም፡በሚደክምበት፡ድካም፡ኹሉ፡ደስ፡ይለው፡ዘንድ፡ነው፤ይህ፡ዕድል፡ፈንታው፡ ነውና።

19፤እግዚአብሔር፡ለሰው፡ኹሉ፡ባለጠግነትንና፡ሀብትን፡መስጠቱ፥ከርሷም፡ይበላና፡ዕድል፡ፈንታውን፡ይወስድ፡ ዘንድ፡በድካሙም፡ደስ፡ይለው፡ዘንደ
ማሠልጠኑ፤ይህ፡የእግዚአብሔር፡ስጦታ፡ነው።
20፤እግዚአብሔር፡በልቡ፡ደስታን፡ስለ፡ሰጠው፡ርሱ፡የሕይወቱን፡ዘመን፡እጅግ፡አያስብም።

___________________መጽሐፈ፡መክብብ፥ምዕራፍ፡6።_________________

ምዕራፍ፡6።

1፤ከፀሓይ፡በታች፡ያየኹት፡ክፉ፡ነገር፡አለ፥ርሱም፡በሰው፡ላይ፡እጅግ፡የከበደ፡ነው።
2፤እግዚአብሔር፡ለሰው፡ሀብትንና፡ጥሪትን፡ክብርንም፡ሰጠው፥ከወደደውም፡ኹሉ፡ለነፍሱ፡አልጐደለውም፤ነገር፡ ግን፥ሌላ፡ሰው፡ይበላዋል፡እንጂ፡ከሰ
ይበላ፡ዘንድ፡እግዚአብሔር፡አላሠለጠነውም፤ይህም፡ከንቱና፡ክፉ፡ደ ዌ፡ነው።
3፤ሰው፡መቶ፡ልጆች፡ቢወልድ፡እጅግ፡ዘመንም፡በሕይወት፡ቢኖር፡ዕድሜውም፡እጅግ፡ዓመት፡ቢኾን፥ነፍሱም፡መልካ ምን፡ባትጠግብ፡መቃብርንም፡
ባያገኝ፥እኔ፡ስለ፡ርሱ፡-ከርሱ፡ይልቅ፡ጭንጋፍ፡ይሻላል፡አልኹ።
4፤በከንቱ፡መጥቷል፡በጨለማ፡ይኼዳል፡ስሙም፡በጨለማ፡ይሸፈናል፤
5፤ደግሞም፡ፀሓይን፡አላየውም፡አላወቀውምም፤ለዚህም፡ከዚያ፡ይልቅ፡ዕረፍት፡አለው።
6፤ሺሕ፡ዓመት፡ኹለት፡ጊዜ፡በሕይወት፡ቢኖር፡መልካምንም፡ባያይ፥ኹሉ፡ወደ፡አንድ፡ስፍራ፡የሚኼድ፡አይደለምን ፧
7፤የሰው፡ድካም፡ኹሉ፡ለአፉ፡ነው፥ነፍሱ፡ግን፡አትጠግብም።
8፤ከሰነፍ፡ይልቅ፡ለጥበበኛ፡ጥቅም፡ምንድር፡ነው፧በሕያዋን፡ፊትስ፡መኼድ፡ለሚያውቅ፡ለድኻ፡ጥቅሙ፡ምንድር፡ ነው፧
9፤በዐይን፡ማየት፡በነፍስ፡ከመቅበዝበዝ፡ይሻላል፤ይህም፡ደግሞ፡ከንቱ፡ነፋስንም፡እንደ፡መከተል፡ነው።
10፤የኾነው፡ስሙ፡አስቀድሞ፡ተጠራ፥ሰውም፡እንደ፡ኾነ፡ታወቀ፤ከርሱ፡ከሚበረታው፡ጋራ፡ይፋረድ፡ዘንድ፡አይች ልም።
11፤ከንቱን፡የሚያበዛ፡ብዙ፡ነገር፡አለና፡ለሰው፡ጥቅሙ፡ምንድር፡ነው፧
12፤ሰው፡በከንቱ፡ወራቱ፡ቍጥርና፡እንደ፡ጥላ፡በሚያሳልፈው፡ዘመኑ፡በሕይወቱ፡ሳለ፡ለሰው፡የሚሻለውን፡የሚያ ውቅ፡ማነው፤ወይስ፡ለሰው፡ከፀሓይ፡
በታች፡ከርሱ፡በኋላ፡የሚኾነውን፡ማን፡ይነግረዋል፧

___________________መጽሐፈ፡መክብብ፥ምዕራፍ፡7።_________________

ምዕራፍ፡7።

1፤ከመልካም፡ሽቱ፡መልካም፡ስም፥ከመወለድ፡ቀንም፡የሞት፡ቀን፡ይሻላል።
2፤ወደግብዣ፡ቤት፡ከመኼድ፡ወደልቅሶ፡ቤት፡መኼድ፡ይሻላል፤ርሱ፡የሰው፡ኹሉ፡ፍጻሜ፡ነውና፥ሕያውም፡የኾነ፡በ ልቡ፡ያኖረዋልና።
3፤ከሣቅ፡ሐዘን፡ይሻላል፥ከፊት፡ሐዘን፡የተነሣ፡ልብ፡ደስ፡ይሠኛልና።
4፤የጠቢባን፡ልብ፡በልቅሶ፡ቤት፡ነው፤የሰነፎች፡ልብ፡ግን፡በደስታ፡ቤት፡ነው።
5፤ሰው፡የሰነፎችን፡ዜማ፡ከሚሰማ፡ይልቅ፡የጠቢባንን፡ተግሣጽ፡መስማት፡ይሻለዋል።
6፤ከድስት፡በታች፡እንደሚቃጠል፡ሾኽ፡ድምፅ፡የሰነፍ፡ሣቅ፡እንዲሁ፡ነው፤ይህም፡ደግሞ፡ከንቱ፡ነው።
7፤ግፍ፡ጠቢቡን፡ያሳብደዋል፤ጉቦም፡ልቡን፡ያጠፋዋል።
8፤የነገር፡ፍጻሜ፡ከመዠመሪያው፡ይሻላል፤ታጋሽም፡ከትዕቢተኛ፡ይሻላል።
9፤በነፍስኽ፡ለቍጣ፡ችኵል፡አትኹን፡ቍጣ፡በሰነፍ፡ብብት፡ያርፋልና።
10፤ከዚህ፡ዘመን፡ይልቅ፡ያለፈው፡ዘመን፡ለምን፡ተሻለ፧ብለኽ፡አትናገር፤የዚህን፡ነገር፡በጥበብ፡አትጠይቅም ና።
11፤ጥበብ፡ከርስት፡ጋራ፡መልካም፡ነው፤ፀሓይንም፡ለሚያዩ፡ሰዎች፡ትርፍን፡ይሰጣል።
12፤የጥበብ፡ጥላ፡እንደ፡ገንዘብ፡ጥላ፡ናትና፤የዕውቀትም፡ብልጫዋ፡ጥበብ፡ገንዘብ፡ላደረጋት፡ሕይወትን፡እን ድትሰጥ፡ነው።
13፤የእግዚአብሔርን፡ሥራ፡ተመልከት፤ርሱ፡ጠማማ፡ያደረገውን፡ማን፡ሊያቀናው፡ይችላል፧
14፤በመልካም፡ቀን፡ደስ፡ይበልኽ፤በክፉም፡ቀን፡ተመልከት፤ሰው፡ከርሱ፡በኋላ፡መርምሮ፡ምንም፡እንዳያገኝ፡እ ግዚአብሔር፡ይህንም፡ያንም፡እንደዚያ
ሠርቷል።
15፤ጻድቅ፡በጽድቁ፡ሲጠፋ፡ኃጥእም፡በክፋቱ፡እጅግ፡ዘመን፡ሲኖር፥ይህን፡ኹሉ፡ከንቱ፡በኾነ፡ዘመኔ፡አየኹ።
16፤እጅግ፡ጻድቅ፡አትኹን፥እጅግ፡ጠቢብም፡አትኹን፥እንዳትጠፋ።
17፤እጅግ፡ክፉ፡አትኹን፥እልከኛም፡አትኹን፥ጊዜኽ፡ሳይደርስ፡እንዳትሞት።
18፤እግዚአብሔርን፡የሚፈራ፡ከኹሉ፡ይወጣልና፥ይህን፡ብትይዝ፡ከዚያም፡ደግሞ፡እጅኽን፡ባታርቅ፡መልካም፡ነው ።
19፤በከተማ፡ከሚኖሩ፡ከዐሥር፡ገዢዎች፡ይልቅ፡ጥበብ፡ጠቢብን፡ታበረታለች።
20፤በምድር፡ላይ፡መልካምን፡የሚሠራ፡ኀጢአትንም፡የማያደርግ፡ጻድቅ፡አይገኝምና።
21፤ባሪያኽ፡ሲረግምኽ፡እንዳትሰማ፡በሚጫወቱበት፡ቃል፡ኹሉ፡ልብኽን፡አትጣል፤
22፤አንተ፡ደግሞ፡ሌላዎችን፡እንደ፡ረገምኽ፡ልብኽ፡ያውቃልና።
23፤ይህን፡ኹሉ፡በጥበብ፡ፈተንኹ፤ጠቢብ፡እኾናለኹ፡አልኹ፥ርሷ፡ግን፡ከእኔ፡ራቀች።

24፤የኾነው፡ራቀ፡እጅግም፡ጠለቀ፤መርምሮ፡የሚያገኘውስ፡ማን፡ነው፤
25፤ዐውቅና፡እመረምር፡ዘንድ፥ጥበብንና፡የነገሩን፡ኹሉ፡መደምደሚያ፡እፈልግ፡ዘንድ፥ኀጢአትም፡ስንፍና፥ስን ፍናም፡እብደት፡እንደ፡ኾነች፡ዐውቅ፡ዘንድ፡እኔ፡በልቤ፡ዞርኹ።
26፤እኔም፡ከሞት፡ይልቅ፡የመረረ፡ነገር፡መርምሬ፡አገኘኹ፤ርሷም፡ልቧ፡ወጥመድና፡መርበብ፡የኾነ፥እጆቿም፡እ ግር፡ብረት፡የኾኑ፡ሴት፡ናት፤በእግዚአብሔር፡ፊት፡መልካም፡የኾነ፡ከርሷ፡ያመልጣል፥ኀጢአተኛ፡ግን፡ይጠመድ ባታል።
27፤አንዱን፡በአንዱ፡ላይ፡ጨምሬ፡ወደ፡ነገሩ፡ኹሉ፡መደምደሚያ፡እደርስ፡ዘንድ፥እንሆ፥ይህን፡ነገር፡አገኘኹ ፡ይላል፡ሰባኪው፤
28፤ነፍሴ፡እስከ፡ዛሬ፡ድረስ፡ትሻታለች፥ነገር፡ግን፥አላገኘኹም፤ከሺሕ፡ወንዶች፡አንድ፡አገኘኹ፥ከነዚያ፡ኹ ሉ፡መካከል፡ግን፡አንዲት፡ሴት፡አላገኘኹም
29፤እግዚአብሔር፡ሰዎችን፡ቅኖች፡አድርጎ፡እንደ፡ሠራቸው፥እንሆ፥ይህን፡ብቻ፡አገኘኹ፤እነርሱ፡ግን፡ብዙ፡ብ ልኀትን፡ፈለጉ።

__________________መጽሐፈ፡መክብብ፥ምዕራፍ፡8።_________________

ምዕራፍ፡8።

1፤እንደ፡ጠቢብ፡የኾነ፡ሰው፡ማን፡ነው፤ነገርንስ፡መተርጐም፡የሚያውቅ፡ማን፡ነው፤የሰው፡ጥበብ፡ፊቱን፡ታበራ ለች፥የፊቱንም፡ድፍረት፡ትለውጣለች።
2፤እኔ፡-በእግዚአብሔር፡መሐላ፡ምክንያት፡የንጉሥን፡ትእዛዝ፡ጠብቅ፡እልኻለኹ።
3፤የወደደውን፡ኹሉ፡ያደርጋልና፥ከፊቱ፡ትወገድ፡ዘንድ፡አትቸኵል፥ክፉንም፡በማድረግ፡አትጽና።
4፤የንጉሥ፡ቃል፡ኀይለኛ፡ነውና፤ይህንስ፡ለምን፡ታደርጋለኽ፤ማን፡ይለዋል፤
5፤ትእዛዝን፡የሚጠብቅ፡ክፉን፡ነገር፡አያውቅም፤የጠቢብም፡ልብ፡ጊዜንና፡ፍርድን፡ያውቃል።
6፤የሰው፡መከራ፡በርሱ፡ላይ፡እጅግ፡ስለ፡ኾነ፡ለነገር፡ኹሉ፡ጊዜና፡ፍርድ፡አለውና።
7፤የሚኾነውንም፡አያውቅም፤እንዴትስ፡እንደሚኾን፡የሚነግረው፡ማን፡ነው፤
8፤መንፈስን፡ለማስቀረት፡በመንፈስ፡ላይ፡ሥልጣን፡ያለው፡ሰው፡የለም፤በሞቱም፡ቀን፡ሥልጣን፡የለውም፤በሰልፍ ም፡ስንብቻ፡የለም፥ኀጢአትም፡ሠሪውን፡አያድነውም።
9፤ይህን፡ኹሉ፡አየኹ፥ከፀሓይም፡በታች፡ወደተደረገው፡ሥራ፡ኹሉ፡ልቤን፡ሰጠኹ፤ሰው፡ሰውን፡ለመጕዳት፡ገዢ፡የ ሚኾንበት፡ጊዜ፡አለ።
10፤እንዲሁም፡ኃጥኣን፡ተቀብረው፡አየኹ፥ወደ፡ዕረፍትም፡ገቡ፤ነገር፡ግን፥ቅን፡አድራጊዎች፡ከቅድስት፡ስፍራ ፡ወጡ፥በከተማዪቱም፡ውስጥ፡ተረሱ፤ይህም፡ደግሞ፡ከንቱ፡ነው።
11፤በክፉ፡ሥራ፡ላይ፡ፈጥኖ፡ፍርድ፡አይፈረድምና፡ስለዚህ፡በሰው፡ልጆች፡ውስጥ፡ልባቸው፡ክፉን፡ለመሥራት፡ጠ ነከረ።
12፤ኀጢአተኛ፡መቶ፡ጊዜ፡ክፉን፡ቢሠራ፡ዘመኑም፡ረዥም፡ቢኾን፥እግዚአብሔርን፡ለሚፈሩት፡በፊቱም፡ለሚፈሩት፡ ደኅንነት፡እንዲኾን፡ዐውቃለኹ፤
13፤ለኃጥእ፡ግን፡ደኅንነት፡የለውም፥በእግዚአብሔርም፡ፊት፡አይፈራምና፡ዘመኑ፡እንደ፡ጥላ፡አትረዝምም።
14፤በምድር፡የሚደረግ፡ከንቱ፡ነገር፡አለ፤በኃጥኣን፡የሚደረገው፡ሥራ፡የሚደርስባቸው፡ጻድቃን፡አሉ፥ለጻድቃ ንም፡የሚደረገው፡ሥራ፡የሚደርስላቸው ኃጥኣን፡አሉ፤ይህም፡ደግሞ፡ከንቱ፡ነው፡አልኹ።
15፤ከሚበላውና፡ከሚጠጣው፡ደስም፡ከሚለው፡በቀር፡ለሰው፡ከፀሓይ፡በታች፡ሌላ፡መልካም፡ነገር፡የለውምና፥እኔ ፡ደስታን፡አመሰገንኹ፤ከፀሓይም፡በታች፡ከድካሙ፡እግዚአብሔር፡በሰጠው፡በሕይወቱ፡ዘመን፡ይህ፡ደስታው፡ከር ሱ፡ጋራ፡ይኖራል።
16፤ጥበብን፡ዐውቅ፡ዘንድ፡በምድር፡የሚኾነውንም፡ድካም፡አይ፡ዘንድ፡ልቤን፡ሰጠኹ፥በቀንና፡በሌሊት፡እንቅል ፍን፡በዐይኑ፡የማያይ፡አለና፤
17፤ከፀሓይም፡በታች፡የተደረገውን፡ሥራ፡መርምሮ፡ያገኝ፡ዘንድ፡ለሰው፡እንዳይቻለው፡የእግዚአብሔርን፡ሥራ፡ ኹሉ፡አየኹ።ሰውም፡ሊፈልግ፡እጅግ ቢደክም፥መርምሮ፡አያገኘውም፤ደግሞ፡ጠቢብ፡ሰው፡-ይህን፡ዐወቅኹ፡ቢል፥ር ሱ፡ያገኘው፡ዘንድ፡አይችልም።

__________________መጽሐፈ፡መክብብ፥ምዕራፍ፡9።_________________

ምዕራፍ፡9።

1፤ጻድቃንና፡ጠቢባን፡ሥራዎቻቸውም፡በእግዚአብሔር፡እጅ፡እንደ፡ኾኑ፥ይህን፡ኹሉ፡እመረምር፡ዘንድ፡በልቤ፡አ ኖርኹ፤ፍቅር፡ወይም፡ጥል፡ቢኾን፡ሰው፡አያውቅም፤ኹሉ፡ወደ፡ፊታቸው፡ነው።
2፤የጻድቁና፡የበደለኛው፥የመልካሙና፡የክፉው፥የንጹሑና፡የርኩሱ፥መሥዋዕትን፡የሚሠዋውና፡የማይሠዋው፥የሰው ፡ኹሉ፡ድርሻው፡አንድ፡ነው፤እን መልካሙ፡ሰው፡እንዲሁ፡ኀጢአተኛው፥እንደ፡መሐለኛው፡ሰው፡እንዲሁ፡መሐላ ን፡የሚፈራው፡ነው።
3፤አንድ፡ድርሻ፡ኹሉን፡እንዲያገኝ፡ከፀሓይ፡በታች፡በተደረገው፡ኹሉ፡ይህ፡ነገር፡ክፉ፡ነው፤ደግሞም፡የሰው፡ ልጆች፡ልብ፡ክፋትን፡ትሞላለች፥በሕይወታቸውም፡ሳሉ፡እብደት፡በልባቸው፡ነው፥ከዚያም፡በኋላ፡ወደ፡ሙታን፡ይ ወርዳሉ።
4፤ያልሞተ፡ውሻ፡ከሞተ፡አንበሳ፡ይሻላልና፥ሰው፡ከሕያዋን፡ኹሉ፡ጋራ፡በአንድነት፡ቢኖር፡ተስፋ፡አለው።
5፤ሕያዋን፡እንዲሞቱ፡ያውቃሉና፤ሙታን፡ግን፡አንዳች፡አያውቁም፤መታሰቢያቸውም፡ተረስቷልና፥ከዚያ፡በኋላ፡ዋ ጋ፡የላቸውም።
6፤ፍቅራቸውና፡ጥላቸው፡ቅንአታቸውም፡በአንድነት፡ጠፍቷል፥ከፀሓይ፡በታችም፡በሚሠራው፡ነገር፡ለዘለዓለም፡ዕ ድል፡ፈንታ፡ከእንግዲህ፡ወዲህ፡የላቸውም።
7፤እግዚአብሔር፡ሥራኽን፡ተቀብሎታልና፥ኺድ፤እንጀራኽን፡በደስታ፡ብላ፥የወይን፡ጠጅኽንም፡በተድላ፡ጠጣ።
8፤ኹልጊዜ፡ልብስኽ፡ነጭ፡ይኹን፤ቅባትም፡ከራስኽ፡ላይ፡አይታጣ።
9፤በሕይወትኽ፥አንተም፡ከፀሓይ፡በታች፡በምትደክምበት፡ድካም፡ይህ፡ዕድል፡ፈንታኽ፡ነውና፥ከንቱ፡በኾነ፡በሕ ይወትኽ፡ዘመን፡ኹሉ፥ከፀሓይ፡በታች

በሰጠኽ፥በከንቱ፡ዘመንኽ፡ዅሉ፥ከምትወዳት፡ሚስትኽ፡ጋራ፡ደስ፡ይበል ኽ።
10፤አንተ፡በምትኼድበት፡በሲኦል፡ሥራና፡ዐሳብ፡ዕውቀትና፡ጥበብ፡አይገኙምና፡እጅኽ፡ለማድረግ፡የምታገኘውን ፡ዅሉ፡እንደ፡ኀይልኽ፡አድርግ።
11፤እኔም፡ተመለስኹ፥ከፀሓይ፡በታችም፡ሩጫ፡ለፈጣኖች፥ሰልፍም፡ለኀያላን፥እንጀራም፡ለጠቢባን፥ባለጠግነትም ፡ለአስተዋዮች፥ሞገስም፡ለዐዋቂዎች
እንዳልኾነ፡አየኹ፤ጊዜና፡ዕድል፡ግን፡ዅሉን፡ይገናኛቸዋል።
12፤ሰውም፡ጊዜውን፡አያውቅም፤በክፉ፡መረብ፡እንደ፡ተጠመዱ፡ዓሣዎች፥በወጥመድም፡እንደ፡ተያዙ፡ወፎች፥እንዲ ሁ፡የሰው፡ልጆች፡በክፉ፡ጊዜ፡
በድንገት፡ሲወድቅባቸው፡ይጠመዳሉ።
13፤ከፀሓይ፡በታችም፡ይህን፡ጥበብ፡አየኹ፥ርሷም፡በእኔ፡ዘንድ፡ታላቅ፡መሰለችኝ።
14፤ታናሽ፡ከተማ፡ነበረች፥ጥቂቶች፡ሰዎችም፡ነበሩባት፤ታላቅ፡ንጉሥም፡መጣባት፡ከበባትም፥ታላቅ፡ግንብም፡ሠ ራባት።
15፤ጠቢብ፡ድኻ፡ሰውም፡ተገኘባት፥ያችንም፡ከተማ፡በጥበቡ፡አዳናት፤ያን፡ድኻ፡ሰው፡ግን፡ማንም፡አላሰበውም።
16፤እኔም።ከኀይል፡ይልቅ፡ጥበብ፡ትበልጣለች፤የድኻው፡ጥበብ፡ግን፡ተናቀች፡ቃሉም፡አልተሰማችም፡አልኹ።
17፤በሰነፎች፡መካከል፡ከሚጮኽ፡ከገዢው፡ጩኸት፡ይልቅ፡የጠቢባን፡ቃል፡በጸጥታ፡ትሰማለች።
18፤ከጦር፡መሣሪያዎች፡ይልቅ፡ጥበብ፡ትሻላለች፤አንድ፡ኀጢአተኛ፡ግን፡ብዙ፡መልካምን፡ያጠፋል።
__________________መጽሐፈ፡መክብብ፥ምዕራፍ፡10።_________________
ምዕራፍ፡10።
1፤የሞቱ፡ዝንቦች፡የተቀመመውን፡የዘይት፡ሽቱ፡ያገሙታል፤እንዲሁም፡ትንሽ፡ስንፍና፡ጥበብንና፡ክብርን፡ያጠፋ ል።
2፤የጠቢብ፡ልብ፡በስተቀኙ፡ነው፥የሰነፍ፡ልብ፡ግን፡በስተግራው፡ነው።
3፤ደግሞም፡ሰነፍ፡በመንገድ፡ሲመላለስ፡ርሱ፡ልብ፡ይጐድለዋል፥የሚያስበውም፡ዅሉ፡ስንፍና፡ነው።
4፤ትዕግሥት፡ታላቁን፡ኀጢአት፡ጸጥ፡ያደርጋልና፥የገዢ፡ቍጣ፡የተነሣብኽ፡እንደ፡ኾነ፡ስፍራኽን፡አትልቀቅ።
5፤ከፀሓይ፡በታች፡ያየኹት፡ክፉ፡ነገር፡አለ፥ርሱም፡ከገዢ፡የሚወጣ፡ስሕተት፡ነው፤
6፤ሰነፍ፡በታላቅ፡ማዕርግ፡ተሾመ፥ባለጠጋዎች፡ግን፡በተዋረደ፡ስፍራ፡ተቀመጡ።
7፤ባሪያዎች፡በፈረስ፡ላይ፡ሲቀመጡ፡መሳፍንትም፡እንደ፡ባሪያዎች፡በምድር፡ላይ፡ሲኼዱ፡አየኹ።
8፤ጕድጓድን፡የሚምስ፡ይወድቅበታል፥ቅጥርንም፡የሚያፈርስን፡እባብ፡ትነድፈዋለች።
9፤ድንጋይን፡የሚፈነቅል፡ይታመምበታል፥ዕንጨትንም፡የሚፈልጥ፡ይጐዳበታል።
10፤ብረት፡ቢደነዝዝ፡ሰውም፡ባይስለው፡ኀይልን፡ሊያበዛ፡ይገ̈ባዋል፤ጥበብ፡ግን፡ሥራውን፡ለማከናወን፡ትጠ ቅመዋለች።
11፤ደጋሚ፡ሳይደግምባት፡እባብ፡ብትነድፍ፡ለደጋሚው፡ትርፍ፡የለውም።
12፤የጠቢብ፡ሰው፡የአፉ፡ቃል፡ሞገስ፡ናት፤የሰነፍ፡ከንፈሮች፡ግን፡ራሱን፡ይውጡታል።
13፤የአፉ፡ቃል፡መዠመሪያ፡ስንፍና፡ነው፥የንግግሩ፡ፍጻሜም፡ክፉ፡እብደት፡ነው።
14፤ሰነፍ፡ቃሉን፡ያበዛል፤ሰው፡ግን፡የሚኾነውን፡አያውቅም፤ከርሱስ፡በዃላ፡የሚኾነውን፡ማን፡ይነግረዋል፧
15፤የሰነፍ፡ሥራ፡ያደክመዋል፡ወደ፡ከተማ፡መኼድ፡አያውቅምና።
16፤ንጉሥሽ፡ሕፃን፡የኾነ፥መኳንንቶችሽም፡ማልደው፡የሚበሉ፥አንቺ፡አገር፡ሆይ፥ወዮልሽ!
17፤ንጉሥሽ፡የከበረ፡ልጅ፡የኾነ፥ለብርታት፡እንጂ፡ለስካር፡ያይደለ፡በጊዜ፡የሚበሉ፡መኳንንት፡ያሉሽ፥አንቺ ፡አገር፡ሆይ፥የተመሰገንሽ፡ነሽ።
18፤ተግባር፡በመፍታት፡ጣራው፡ይዘብጣል፥በእጅም፡መታከት፡ቤት፡ያፈሳ̈ል።
19፤እንጀራን፡ለሣቅ፡የወይን፡ጠጅንም፡ለሕይወት፡ደስታ፡ያደርጉታል፥ዅሉም፡ለገንዘብ፡ይገዛል።
20፤የሰማይ፡ወፍ፡ቃሉን፡ይወስደዋልና፥ባለክንፎችም፡ነገሩን፡ይናገራሉና፡በልብኽ፡ዐሳብ፡እንኳ፡ቢኾን፡ንጉ ሥን፡አትስደብ፥በመኝታ፡ቤትኽም፡
ባለጠጋን፡አትስደብ።
__________________መጽሐፈ፡መክብብ፥ምዕራፍ፡11።_________________
ምዕራፍ፡11።
1፤እንጀራኽን፡በውሃ፡ፊት፡ላይ፡ጣለው፥ከብዙ፡ቀን፡በዃላ፡ታገኘዋለኽና።
2፤ለሰባት፡ደግሞም፡ለስምንት፡ዕድል፡ፈንታን፡ክፈል፥በምድር፡ላይ፡የሚኾነውን፡ክፉ፡ነገር፡ምን፡እንደ፡ኾነ ፡አታውቅምና።
3፤ደመናት፡ዝናብ፡በሞሉ፡ጊዜ፡በምድር፡ላይ፡ያፈሡታል፤ዛፍም፡ወደ፡ደቡብ፡ወይም፡ወደ፡ሰሜን፡ቢወድቅ፥ዛፉ ፡በወደቀበት፡ስፍራ፡በዚያ፡ይኖራል።
4፤ነፋስን፡የሚጠባበቅ፡አይዘራም፥ደመናንም፡የሚመለከት፡አያጭድም።
5፤የነፋስ፡መንገድ፡እንዴት፡እንደ፡ኾነች፡ዐጥንትም፡በእርጕዝ፡ሆድ፡እንዴት፡እንድትዋደድ፡እንደማታውቅ፥እ ንዲሁም፡ዅሉን፡የሚሠራውን፡
የእግዚአብሔርን፡ሥራ፡አታውቅም።
6፤ወይም፡ይህ፡ወይም፡ያ፡ማናቸው፡እንዲበቅል፡ወይም፡ኹለቱ፡መልካም፡እንዲኾኑ፡አታውቅምና፡በማለዳ፡ዘርኽን ፡ዝራ፥በማታም፡እጅኽን፡አትተወ
7፤ብርሃን፡ጣፋጭ፡ነው፥ፀሓይንም፡ማየት፡ለዐይን፡መልካም፡ነው።
8፤ሰው፡ብዙ፡ዘመን፡በሕይወት፡ቢኖር፡በዅሉም፡ደስ፡ይበለው፤ኾኖም፡የጨለማውን፡ዘመን፡ያስብ፥ብዙ፡ቀን፡ይኾ ናልና።የሚመጣው፡ነገር፡ዅሉ፡ከ

ነው።
9፤አንተ፡ጐበዝ፥በጕብዝናኽ፡ደስ፡ይበልኽ፥በጕብዝናኽም፡ወራት፡ልብኽን፡ደስ፡ይበለው፥በልብኽም፡መንገድ፡ዐ ይኖችኽም፡በሚያዩት፡ኺድ፤ዳሩ፡
ስለዚህ፡ነገር፡ኹሉ፡እግዚአብሔር፡ወደ፡ፍርድ፡እንዲያመጣኽ፡ዕወቅ።
10፤ሕፃንነትና፡ጕብዝና፡ከንቱዎች፡ናቸውና፥ከልብኽ፡ሐዘንን፡አርቅ፥ከሰውነትኽም፡ክፉን፡ነገር፡አስወግድ።
____________________መጽሐፈ፡መክብብ፥ምዕራፍ፡12።____________________
ምዕራፍ፡12።
1፤የጭንቀት፡ቀን፡ሳይመጣ፡በጕብዝናኽ፡ወራት፡ፈጣሪኽን፡ዐስብ፤ደስ፡አያሠኙም፡የምትላቸውም፡ዓመታት፡ሳይደ ርሱ፤
2፤ፀሓይና፡ብርሃን፡ጨረቃና፡ከዋክብትም፡ሳይጨልሙ፥ደመናትም፡ከዝናብ፡በኋላ፡ሳይመለሱ፤
3፤ቤት፡ጠባቂዎች፡በሚንቀጠቀጡበት፥ኀያላን፡ሰዎችም፡በሚጐብጡበት፥ጥቂቶች፡ኾነዋልና፥ፈጪታዎች፡ሥራ፡በሚፈ ቱበት፥በመስኮትም፡ኾነው፡
የሚመለከቱ፡በሚጨልሙበት፥በአደባባይም፡ደጆቹ፡በሚዘጉበት፡ቀን፤
4፤የወፍጮ፡ድምፅ፡ሲላሽ፥ከወፍ፡ድምፅ፡የተነሣ፡ሰው፡ሲነሣ፥ዜማም፡የሚጮኹ፡ሴቶች፡ልጆች፡ኹሉ፡ዝግ፡ሲሉ፤
5፤ከፍ፡ያለውን፡ደግሞ፡ሲፈሩ፥ድንጋጤም፡በመንገድ፡ላይ፡ሲኾን፤ለውዝም፡ሲያብብ፥አንበጣም፡እንደ፡ሸክም፡ሲ ከብድ፥ፈቃድም፡ሲጠፋ፤ሰው፡
ወደዘለዓለም፡ቤት፡ሲኼድ፥አልቃሾችም፡በአደባባይ፡ሲዞሩ፤
6፤የብር፡ድሪ፡ሳይበጠስ፥የወርቅም፡ኵስኵስት፡ሳይሰበር፥ማድጋውም፡በምንጭ፡አጠገብ፡ሳይከሰከስ፥መንኰራኵሩ ም፡በጕድጓድ፡ላይ፡ሳይሰበር፥
7፤ዐፈርም፡ወደነበረበት፡ምድር፡ሳይመለስ፥ነፍስም፡ወደሰጠው፡ወደ፡እግዚአብሔር፡ሳይመለስ፡ፈጣሪኽን፡ዐስብ ።
8፤ሰባኪው፡-ከንቱ፥ከንቱ፤ኹሉ፡ከንቱ፡ነው፡ይላል።
9፤ሰባኪውም፡ጠቢብ፡ስለ፡ኾነ፡ለሕዝቡ፡ዕውቀትን፡አስተማረ፤ርሱም፡ብዙ፡ምሳሌዎችን፡መረመረና፡ፈላለገ፡አስ ማማም።
10፤ሰባኪው፡ያማረውን፡በቅንም፡የተጻፈውን፡እውነተኛውን፡ቃል፡መርምሮ፡ለማግኘት፡ፈለገ።
11፤የጠቢባን፡ቃል፡እንደ፡በሬ፡መውጊያ፡ነው፥የተሰበሰቡትም፡ካንድ፡እረኛ፡የተሰጡት፡ቃላት፡እንደ፡ተቸነከ ሩ፡ችንካሮች፡ናቸው።
12፤ከዚህም፡ኹሉ፡በላይ፥ልጄ፡ሆይ፥ተግሣጽን፡ስማ፤ብዙ፡መጻሕፍትን፡ማድረግ፡ፍጻሜ፡የለውም፥እጅግም፡ምርም ር፡ሰውነትን፡ያደክማል።
13፤የነገሩን፡ኹሉ፡ፍጻሜ፡እንስማ፤ይህ፡የሰው፡ኹለንተናው፡ነውና፤እግዚአብሔርን፡ፍራ፥ትእዛዙንም፡ጠብቅ።
14፤እግዚአብሔር፡ሥራን፡ኹሉ፡የተሰወረውንም፡ነገር፡ኹሉ፥መልካምም፡ቢኾን፡ክፉም፡ቢኾን፥ወደ፡ፍርድ፡ያመጣ ዋልና፨

# ማሕልየ፥መሓልይ፥ዘሰሎሞን።

(ክለሳ.1.20020507)

__________________ማሕልየ፡መሓልይ፡ዘሰሎሞን፥ምዕራፍ፡1።__________________

ምዕራፍ፡1።

1፤ከመዝሙር፡ኹሉ፡የሚበልጥ፡የሰሎሞን፡መዝሙር።

2፤በአፉ፡መሳም፡ይሳመኝ፥ፍቅርኽ፡ከወይን፡ጠጅ፡ይልቅ፡መልካም፡ነውና።

3፤ዘይትኽ፡መልካም፡መዐዛ፡አለው፤ስምኽ፡እንደሚፈሰ፡ዘይት፡ነው፤ስለዚህ፥ደናግል፡ወደዱኽ።

4፤ሳበኝ፥ከአንተም፡በዃላ፡እንሮጣለን፤ንጉሡ፡ወደ፡ቤቱ፡አገባኝ፡ባንተ፡ደስ፡ይለናል፥ሐሤትም፡እናደርጋለን ፤ከወይን፡ጠጅ፡ይልቅ፡ፍቅርኽን፡እናስባለ
በቅንነት፡ይወዱኻል።

5፤እናንተ፡የኢየሩሳሌም፡ቈነዣዥት፡ሆይ፥እኔ፡ጥቍር፡ነኝ፤ነገር፡ግን፥ውብ፡ነኝ፥እንደ፡ቄዳር፡ድንኳኖች፡እ ንደ፡ሰሎሞንም፡መጋረጃዎች።

6፤ፀሓይ፡መልኬን፡አክስሎታልና፤ጥቍር፡ስለ፡ኾንኹ፡አትዩኝ፤የእናቴ፡ልጆች፡ተጣሉኝ፥የወይን፡ቦታዎችንም፡ጠ ባቂ፡አደረጉኝ፤ነገር፡ግን፥የእኔን፡ወይ
ቦታ፡አልጠበቅኹም።

7፤ነፍሴ፡የወደደችኽ፡አንተ፡ንገረኝ፤ወዴት፡ታሰማራለኽ፤በቀትርስ፡ጊዜ፡ወዴት፡ትመስጋለኽ፤ስለ፡ምንስ፡ከባ ልንጀራዎችኽ፡መንጋዎች፡በዃላ፡
እቅበዘበዛለኹ፤

8፤አንቺ፡በሴቶች፡ዘንድ፡የተዋብሽ፡ሆይ፥ያላወቅሽ፡እንደ፡ኾነ፡የመንጋዎችን፡ፍለጋ፡ተከትለሽ፡ውጪ፥የፍየል ፡ግልገሎችሽንም፡በእረኛዎች፡ድንኳኖች፡
አጠገብ፡አሰማሪ።

9፤ወዳጄ፡ሆይ፥በፈርዖን፡ሠረገላዎች፡እንዳለ፡ፈረስ፡መሰልኹሽ።

10፤የጒንጭሽ፡ውበት፡በከበረ፡ሉል፥ዐንገትሽም፡በዕንቍ፡ድሪ፡ያማረ፡ነው።

11፤ባለብር፡ጒብጒብ፡የኾነ፡የወርቅ፡ጠልሰም፡እናደርግልሻለን።

12፤ንጉሡ፡በማእዱ፡ሳለ፥የእኔ፡ናርዶስ፡መዐዛውን፡ሰጠ።

13፤ውዴ፡ለእኔ፡በጡቶቼ፡መካከል፡እንደሚያርፍ፡እንደ፡ተቋጠረ፡ከርቤ፡ነው።

14፤ውዴ፡ለእኔ፡በዐይንጋዲ፡ወይን፡ቦታ፡እንዳለ፡እንደ፡አበባ፡ዕቅፍ፡ነው።

15፤ወዳጄ፡ሆይ፥እንሆ፥ውብ፡ነሽ፤እንሆ፥አንቺ፡ውብ፡ነሽ፤ዐይኖችሽም፡እንደ፡ርግቦች፡ናቸው።

16፤ውዴ፡ሆይ፥እንሆ፥አንተ፡ውብ፡ነኽ፥መልከ፡መልካምም፡ነኽ፤ዐልጋችንም፡ለምለም፡ነው።

17፤የቤታችን፡ሠረገላ፡የዝግባ፡ዛፍ፡ነው፥የጣሪያችንም፡ማዋቀሪያ፡የጥድ፡ዛፍ፡ነው።

__________________ማሕልየ፡መሓልይ፡ዘሰሎሞን፥ምዕራፍ፡2።__________________

ምዕራፍ፡2።

1፤እኔ፡የሳሮን፡ጽጌ፡ረዳ፡የቈላም፡አበባ፡ነኝ።

2፤በሾኽ፡መካከል፡እንዳለ፡የሱፍ፡አበባ፥እንዲሁ፡ወዳጄ፡በቈነዣዥት፡መካከል፡ናት።

3፤በዱር፡እንዳለ፡እንኮይ፥እንዲሁ፡ውዴ፡በልጆች፡መካከል፡ነው።ከጥላው፡በታች፡እጅግ፡ወድጄ፡ተቀመጥኹ፥ፍሬ ውም፡በጒረሮዬ፡ጣፋጭ፡ነው።

4፤ወደወይን፡ጠጁም፡ቤት፡አገባኝ፥በእኔ፡ላይ፡ያለው፡ዐላማውም፡ፍቅር፡ነው።

5፤በዘቢብም፡አጽናኑኝ፥በእንኮይ፡አበረታቱኝ፥በፍቅሩ፡ተነድፌ፡ታምሜያለኹና።

6፤ግራው፡ከራሴ፡በታች፡ናት፥ቀኙም፡ታቅፈኛለች።

7፤እናንተ፡የኢየሩሳሌም፡ቈነዣዥት፡ሆይ፥ርሱ፡እስኪፈልግ፡ድረስ፥ፍቅርን፡እንዳታስነሡትና፡እንዳታነሣሡት፡ በሚዳቋ፡በምድረ፡በዳም፡ዋላ፡
አምላችኋለኹ።

8፤እንሆ፥የውዴ፡ቃል! በተራራዎች፡ላይ፡ሲዘል፥በኰረብታዎችም፡ላይ፡ሲወረወር፡ይመጣል።

9፤ውዴ፡ሚዳቋን፡ወይም፡የዋላን፡እንቦሳ፡ይመስላል፤እንሆ፥በመስኮቶች፡ሲጐበኝ፥በዐይነ፡ርግብም፡ሲመለከት፥ ርሱ፡ከቅጥራችን፡በዃላ፡ቆሟል።

10፤ውዴ፡እንዲህ፡ብሎ፡ተናገረኝ፡-ወዳጄ፡ሆይ፥ተነሺ፤ውበቴ፡ሆይ፥ነዪ።

11፤እንሆ፥ክረምት፡ዐለፈ፥ዝናቡም፡ዐልፎ፡ኼደ።

12፤አበባዎች፡በምድር፡ላይ፡ተገለጡ፥የዜማም፡ጊዜ፡ደረሰ፥የቍርዬውም፡ቃል፡በምድራችን፡ተሰማ።

13፤በለሱ፡ጐመራ፥ወይኖችም፡አበቡ፡መዐዛቸውንም፡ሰጡ፤ወዳጄ፡ሆይ፥ተነሺ፤ውበቴ፡ሆይ፥ነዪ።

14፤በአለት፡ንቃቃትና፡በገደል፡መሸሸጊያ፡ያለሽ፡ርግብ፡ሆይ፥ቃልሽ፡መልካም፡ፊትሽም፡ያማረ፡ነውና፥መልክሽ ን፡አሳዪኝ፥ድምፅሽንም፡አሰሚኝ።

15፤ወይናችን፡አብቢልና፥የወይናችንን፡ቦታ፡የሚያጠፉትን፡ቀበሮዎች፥ጥቃቅኑን፡ቀበሮዎች፡አጥምዱችኹ፡ያዙል ን።
16፤ውዴ፡የእኔ፡ነው፥እኔም፡የርሱ፡ነኝ፤በሱፍ፡አበባዎች፡መካከልም፡መንጋውን፡ያሰማራል።
17፤ውዴ፡ሆይ፥ቀኑ፡እስኪነፍስ፥ጥላውም፡እስኪሸሽ፡ድረስ፡ተመለስ፤በቅመም፡ተራራ፡ላይ፡ሚዳቋውን፡ወይም፡የ ዋላውን፡እንቦሳ፡ምሰል።

ማሕልየ፡መሓልይ፡ዘሰሎሞን፥ምዕራፍ፡3።

ምዕራፍ፡3።
1፤ሌሊት፡በምንጣፌ፡ላይ፡ነፍሴ፡የወደደችውን፡ፈለግኹት፤ፈለግኹት፡አላገኘኹትም።
2፤እነሣለኹ፡በከተማዪቱም፡እዞራለኹ፥ነፍሴ፡የወደደችውን፡በጐዳናና፡በአደባባይ፡እፈልጋለኹ፤ፈለግኹት፡አላ ገኘኹትም።
3፤ከተማዪቱን፡የሚዞሩት፡ጠባቂዎች፡አገኙኝ፤ነፍሴ፡የወደደችውን፡አያችኹትን፡አልኋቸውም።
4፤ከነርሱም፡ጥቂት፡እልፍ፡ብዬ፡ነፍሴ፡የወደደችውን፡አገኘኹት፥ያዝኹትም፡ወደእናቴም፡ቤት፡ወደወላጅ፡እናቴ ም፡ዕልፍኝ፡እስካገባው፡ድረስ፡አልተውኹትም።
5፤እናንተ፡የኢየሩሳሌም፡ቈነዣዥርት፡ሆይ፥ርሱ፡እስኪፈልግ፡ድረስ፥ፍቅርን፡እንዳታስነሡትና፡እንዳታነሣሡት፡ በሚዳቋ፡በምድረ፡በዳም፡ዋላ፡አምላችኋለኹ።
6፤መዐዛም፡እንደ፡ከርቤና፡እንደ፡ዕጣን፡የኾነችው፥ከልዩ፡ከነጋዴ፡ቅመም፡ኹሉ፡የኾነችው፥ይህች፡ከምድረ፡በ ዳ፡እንደ፡ጢስ፡ምሰሶ፡የወጣችው፡ማን፡ናት፤
7፤እንሆ፥የሰሎሞን፡ዐልጋ፡ናት፤ከእስራኤል፡ኀያላን፡ስድሳ፡ኀያላን፡በዙሪያው፡ናቸው።
8፤ኹሉም፡ሰይፍ፡የያዙ፡ሰልፈኞዎች፡ናቸው፤በሌሊት፡ከሚወድቀው፡ፍርሀት፡የተነሣ፡ሰው፡ኹሉ፡ሰይፉ፡በወገቡ፡ አለ።
9፤ንጉሡ፡ሰሎሞን፡መሸከሚያን፡ከሊባኖስ፡ዕንጨት፡ለራሱ፡አሠራ።
10፤ምሰሶዎቹን፡የብር፥መደገፊያውንም፡የወርቅ፥መቀመጫውንም፡ሐምራዊ፡ግምጃ፡አደረገ፤ውስጡ፡በኢየሩሳሌም፡ ቈነዣዥርት፡ፍቅር፡የተለበጠ፡ነወ
11፤እናንተ፡የጽዮን፡ቈነዣዥርት፥ውጡ፤እናቱ፡በሰርጉ፡ቀንና፡በልቡ፡ደስታ፡ቀን፡ያደረገችለትን፡አክሊል፡ደፍ ቶ፡ንጉሥ፡ሰሎሞንን፡እዩ።

ማሕልየ፡መሓልይ፡ዘሰሎሞን፥ምዕራፍ፡4።

ምዕራፍ፡4።
1፤ወዳጄ፡ሆይ፥እንሆ፥ውብ፡ነሽ፤እንሆ፥አንቺ፡ውብ፡ነሽ፤በዐይነ፡ርግብ፡መሸፈኛሽ፡ውስጥ፡ዐይኖችሽ፡እንደ፡ ርግቦች፡ናቸው፤ጠጕርሽ፡በገለዓድ፡ተራራ እንደሚወርድ፡እንደ፡ፍየል፡መንጋ፡ነው።
2፤ጥርሶችሽ፡ታጥበው፡እንደ፡ተሸለቱ፡ኹሉም፡መንታ፡እንደ፡ወለዱ፡ከነርሱም፡መካን፡እንደሌለባቸው፡መንጋዎች ፡ናቸው።
3፤ከንፈሮችሽ፡እንደ፡ቀይ፡ሐር፡ፈትል፡ናቸው፥አፍሽም፡ያማረ፡ነው፤በዐይነ፡ርግብ፡መሸፈኛሽ፡ውስጥ፡ጕንጭና ፡ጕንጭሽ፡እንደ፡ተከፈለ፡ሮማን፡ናቸወ
4፤ዐንገትሽ፡ለሰልፍ፡ዕቃ፡መስቀያ፡እንደ፡ተሠራው፡እንደ፡ዳዊት፡ግንብ፡ነው፤ሺሕ፡ጋሻ፡የኀያላንም፡መሣሪያ ፡ኹሉ፡ተንጠልጥሎበታል።
5፤ኹለቱ፡ጡቶችሽ፡መንታ፡እንደ፡ተወለዱ፥በሱፍ፡አበባ፡መካከል፡እንደሚሰማሩ፡እንደ፡ሚዳቋ፡ግልገሎች፡ናቸው ።
6፤ቀኑ፡እስኪነፍስ፡ጥላውም፡እስኪያልፍ፡ድረስ፥ወደከርቤው፡ተራራ፡ወደዕጣኑም፡ኰረብታ፡እኼዳለኹ።
7፤ወዳጄ፡ሆይ፥ኹለንተናሽ፡ውብ፡ነው፥ነውርም፡የለብሽም።
8፤ሙሽራዬ፡ሆይ፥ከሊባኖስ፡ከእኔ፡ጋራ፡ነዪ፤ከሊባኖስ፡ከእኔ፡ጋራ፡ነዪ፤ከአማና፡ራስ፡ከሳኔርና፡ከኤርሞን፡ ራስ፥ከአንበሳዎች፡መኖሪያ፡ከነብሮችም፡ተራ ተመልከች።
9፤እኅቴ፡ሙሽራ፡ሆይ፥ልቤን፡በደስታ፡አሳበድሽው፤አንድ፡ጊዜ፡በዐይኖችሽ፥ከዐንገትሽ፡ድሪ፡በአንዱ፡ልቤን፡ በደስታ፡አሳበድሽው።
10፤እኅቴ፡ሙሽራ፡ሆይ፥ፍቅርሽ፡እንዴት፡መልካም፡ነው! ፍቅርሽ፡ከወይን፡ጠጅ፡ይልቅ፡እንዴት፡ይሻላል! የዘይትሽም፡መዐዛ፡ከሽቱ፡ኹሉ!
11፤ሙሽራዬ፡ሆይ፥ከከንፈሮችሽ፡ማር፡ይንጠበጠባል፤ከምላስሽ፡በታች፡ማርና፡ወተት፡አለ፥የልብስሽም፡መዐዛ፡ እንደ፡ሊባኖስ፡ሽታ፡ነው።
12፤እኅቴ፡ሙሽራ፡የተቈለፈ፡ገነት፥የተዘጋ፡ምንጭ፡የታተመም፡ፈሳሽ፡ናት።
13፤ቡቃያሽ፡ሮማንና፡የተመረጠ፡ፍሬ፥ቆዕ፡ከናርዶስ፡ጋራ፡ያለበት፡ገነት፡ነው፥
14፤ናርዶስ፡ከቀጋ፡ጋራ፥የሽቱ፡ሣርና፡ቀረፋ፥ከልዩ፡ልዩ፡ዕጣን፡ጋራ፥ከርቤና፡ሬት፡ከክቡር፡ሽቱ፡ኹሉ፡ጋራ ።
15፤አንቺ፡የገነት፡ምንጭ፥የሕይወት፡ውሃ፡ጉድጓድ፥ከሊባኖስም፡የሚፈሼ፡ወንዝ፡ነሽ።
16፤የሰሜን፡ነፋስ፡ሆይ፥ተነሥ፥የደቡብም፡ነፋስ፡ና፤በገነቴ፡ላይ፡ንፈስ፥ሽቱውም፡ይፍሰስ፤ውዴ፡ወደ፡ገነቱ ፡ይግባ፥መልካሙንም፡ፍሬ፡ይብላ።

ማሕልየ፡መሓልይ፡ዘሰሎሞን፥ምዕራፍ፡5።

ምዕራፍ፡5።
1፤እኅቴ፡ሙሽራዬ፡ሆይ፥ወደ፡ገነቴ፡ገባኹ፥ከርቤዬን፡ከሽቱዬ፡ጋራ፡ለቀምኹ፥እንጀራዬን፡ከማሬ፡ጋራ፡በላኹ፥ የወይን፡ጠጄን፡ከወተቴ፡ጋራ፡ጠጣኹ። ባልንጀራዎቼ፡ሆይ፥ብሉ፤ወዳጆ፡ሆይ፥ጠጪ፤እስክትረኪ፡ድረስ፡ጠጪ።
2፤እኔ፡ተኝቻለኹ፥ልቤ፡ግን፡ነቅቷል፤የውዴ፡ቃል፡ነው፥ርሱም፡ደጁን፡ይመታል፤እኅቴ፥ወዳጄ፥ርግቤ፥መደምደሚ ያዬ፡ሆይ፥በራሴ፡ጠል፥በቈንዳላዬ የሌሊት፡ነጠብጣብ፡ሞልቶበታልና፥ክፈቺልኝ።
3፤ቀሚሴን፡አወለቅኹ፤እንዴት፡እለብሰዋለኹ፤እግሬን፡ታጠብኹ፤እንዴት፡አሳድፈዋለኹ፤

4፤ውዴ፡እጁን፡በቀዳዳ፡ሰደደ፥አንዠቴም፡ስለ፡ርሱ፡ታወከ።

5፤ለውዴ፡እከፍትለት፡ዘንድ፡ተነሣኹ፤እጆቼ፡በደጅ፡መወርወሪያ፡ላይ፡ከርቤን፡አፈሰሱ፥ጣቶቼ፡ፈሳሹን፡ከርቤ ፡አንጠበጠቡ።

6፤ለውዴ፡ከፈትኹለት፥ውዴ፡ግን፡ፈቀቅ፡ብሎ፡ዐልፎ፡ነበር።ነፍሴ፡ከቃሉ፡የተነሣ፡ደነገጠች፤ፈለግኹት፥አላገ ኘኹትም፤ጠራኹት፥አልመለሰልኝም።

7፤ከተማዪቱን፡የሚዞሩት፡ጠባቂዎች፡አገኙኝ፤መቱኝ፥አቈሰሉኝም፤ቅጥር፡ጠባቂዎችም፡የዐይነ፡ርግብ፡መሸፈኛዬ ን፡ወሰዱት።

8፤እናንተ፡የኢየሩሳሌም፡ቈነዣዥት፡ሆይ፥አምላችኋለኹ፤ውዴን፡ያገኛችኹት፡እንደ፡ኾነ፥እኔ፡ከፍቅር፡የተነሣ ፡መታመሜን፡ንገሩት።

9፤አንቺ፡በሴቶች፡ዘንድ፡የተዋብሽ፡ሆይ፥ከሌላ፡ወዳጅ፡ይልቅ፡ውድሽ፡ማን፡ነው፤ይህን፡የሚያኽል፡አምለሽናል ና፥ከሌላ፡ወዳጅ፡ይልቅ፡ውድሽ፡ማን፡ነ

10፤ውዴ፡ነጭና፡ቀይ፡ነው፥ከእልፍ፡የተመረጠ፡ነው።

11፤ራሱ፡ምዝምዝ፡ወርቅ፡ነው፤ቈንዳላው፡የተዝረፈረፈ፡ነው፥እንደ፡ቊራ፡ጥቊረትም፡ጥቊር፡ነው።

12፤ዐይኖቹ፡በሙሉ፡ፈሳሽ፡አጠገብ፡እንዳሉ፡በወተት፡እንደ፡ታጠቡ፡በፈሳሽ፡ውሃ፡አጠገብ፡እንደ፡ተቀመጡ፡እ ንደ፡ርግቦች፡ናቸው።

13፤ጕንጬና፡ጕንጩ፡የሽቱ፡መደብ፡ዕርከን፡እንዳለበት፡እንደ፡ሽቱ፡አትክልት፡ናቸው፤ከንፈሮቹ፡እንደ፡አበባ ዎች፡ናቸው፥የሚፈሽ፡ከርቤንም፡ያንጠበጥባሉ።

14፤እጆቹ፡የቢረሌ፡ፈርጥ፡እንዳለበት፡እንደ፡ወርቅ፡ቀለበት፡ናቸው፤አካሉ፡ብልኀተኛ፡እንደ፡ሠራው፡በሰንፔ ር፡እንዳጌጠ፡እንደ፡ዝኆን፡ጥርስ፡ነው።

15፤እግሮቹ፡በምዝምዝ፡ወርቅ፡እንደ፡ተመሠረቱ፡እንደ፡እብነ፡በረድ፡ምሰሶዎች፡ናቸው፤መልኩ፡እንደ፡ሊባኖስ ና፡እንደ፡ዝግባ፡ዛፍ፡መልካም፡ነው።

16፤አፉ፡እጅግ፡ጣፋጭ፡ነው፥ርሱም፡ፈጽሞ፡ያማረ፡ነው፤እናንተ፡የኢየሩሳሌም፡ቈነዣዥት፡ሆይ፥ውዴ፡ይህ፡ነው ፥ባልንጀራዬም፡ይህ፡ነው።

____________________ማሕልየ፡መሓልይ፡ዘሰሎሞን፥ምዕራፍ፡6።____________________

ምዕራፍ፡6።

1፤አንቺ፡በሴቶች፡ዘንድ፡የተዋብሽ፡ሆይ፥ከአንቺ፡ጋራ፡እንፈልገው፡ዘንድ፡ውድሽ፡ወዴት፡ኼደ፤ውድሽስ፡ወዴት ፡ፈቀቅ፡አለ፤

2፤ውዴ፡በገነቱ፡መንጋውን፡ያሰማራ፡ዘንድ፡አበባውንም፡ይሰበስብ፡ዘንድ፡ወደሽቱ፡መደብ፡ወደ፡ገነቱ፡ወረደ።

3፤እኔ፡የውዴ፡ነኝ፡ውዴም፡የእኔ፡ነው፤በሱፉ፡አበባ፡መካከል፡መንጋውን፡ያሰማራል።

4፤ወዳጄ፡ሆይ፥እንደ፡ቴርሳ፡ውብ፡ነሽ፥እንደ፡ኢየሩሳሌምም፡ያማርሽ፡ነሽ፤ዐላማ፡ይዞ፡እንደ፡ተሰለፈ፡ሰራዊ ት፡ታስፈሪያለሽ።

5፤አውከውኛልና፥ዐይኖችሽን፡ከፊቴ፡መልሺ፤ጠጕርሽ፡ከገለዓድ፡እንደ፡ወረደ፡እንደ፡ፍየል፡መንጋ፡ነው።

6፤ጥርሶችሽ፡ታጥበው፡እንደወጡ፡ዅሉ፡መንታ፡እንደወለዱ፡ከነርሱም፡መካን፡እንደሌለባቸው፡መንጋዎች፡ናቸው።

7፤በዐይነ፡ርግብ፡መሸፈኛሽ፡ውስጥ፡ጕንጭና፡ጕንጭሽ፡እንደ፡ተከፈለ፡ሮማን፡ናቸው።

8፤ስድሳ፡ንግሥታት፣ሰማንያም፡ቁባቶች፣ቊጥር፡የሌላቸውም፡ቈነዣዥት፡አሉ።

9፤ርግቤ፡መደምደሚያዬም፡አንዲት፡ናት፤ለእናቷ፡አንዲት፡ናት፥ለወለደቻትም፡የተመረጠች፡ናት።ቈነዣዥትም፡አ ይተው፡አሞገሷት፥ንግሥታትና፡ቁባቶችም፡አመሰገኗት።

10፤ይህች፡እንደ፡ማለዳ፡ብርሃን፡የምትጐበኝ፥እንደ፡ጨረቃ፡የተዋበች፥እንደ፡ፀሓይም፡የጠራች፥ዐላማ፡ይዞ፡ እንደ፡ተሰለፈ፡ሰራዊት፡የምታስፈራ፡ማን ናት፤

11፤የወንዙን፡ዳር፡ልምላሜ፡አይ፡ዘንድ፥ወይኑ፡አብቦ፣ሮማኑም፡አፍርቶ፡እንደ፡ኾነ፡እመለከት፡ዘንድ፡ወደገ ውዝ፡ገነት፡ወረድኹ።

12፤ሳላውቅ፡ነፍሴ፡በከበረው፡ሠረገላ፡ላይ፡አስቀመጠችኝ።

____________________ማሕልየ፡መሓልይ፡ዘሰሎሞን፥ምዕራፍ፡7።____________________

ምዕራፍ፡7።

1፤አንቺ፡ሱላማጢስ፡ሆይ፥ተመለሽ፥ተመለሽ፤እናይሽ፡ዘንድ፡ተመለሽ፥ተመለሽ።በሱላማጢስ፡ምን፡ታያላችኹ፤ርሷ ፡እንደ፡መሃናይም፡ዘፈን፡ናት።

2፤አንቺ፡የመኰንን፡ልጅ፡ሆይ፥እግሮችሽ፡በጫማ፡ውስጥ፡እንዴት፡ውቦች፡ናቸው! ዳሌዎችሽስ፡በአንጥረኛ፡እጅ፡እንደ፡ተሠሩ፡እንደ፡ዕንቊዎች፡ይመስላሉ።

3፤ዕንብርትሽ፡የወይን፡ጠጅ፡እንደማይጐድልበት፡እንደ፡ተነጠጠ፡ጽዋ፡ነው፤ሆድሽ፡እንደ፡ስንዴ፡ክምር፥በአበ ባም፡እንደ፡ታጠረ፡ነው።

4፤ኹለቱ፡ጡቶችሽ፡እንደ፡ኹለቱ፡መንታ፡እንደ፡ሚዳቋ፡ግልገሎች፡ናቸው።

5፤ዐንገትሽ፡እንደ፡ዝኆን፡ጥርስ፡ግንብ፡ነው፤ዐይኖችሽ፡በሐሴቦን፡ውስጥ፡በባትረቢ፡በር፡አጠገብ፡እንደ፡ው ሃ፡ኵሬዎች፡ናቸው፤አፍንጫሽ፡ወደደማስቆ አፋዛዥ፡እንደሚመለከት፡እንደ፡ሊባኖስ፡ግንብ፡ነው።

6፤ራስሽ፡እንደ፡ቀርሜሎስ፡ተራራ፡በላይሽ፡ነው፤የራስሽም፡ጠጕር፡እንደ፡ሐምራዊ፡ሐር፡ነው፤ንጉሡ፡በሹርባው ፡ታስሯል።

7፤ወዳጄ፡ሆይ፥እንዴት፡የተዋብሽ፡ነሽ! እንዴትስ፡ደስ፡ታሠኛለሽ!

8፤ይህ፡ቁመትሽ፡የዘንባባ፡ዛፍ፡ይመስላል፥ጡቶችሽም፡የወይን፡ዘለላ፡ይመስላሉ።

9፤ወደዘንባባው፡ዛፍ፡እወጣለኹ፡ጫፎቿንም፡እይዛለኹ፡አልኹ፤ጡቶችሽ፡እንደ፡ወይን፡ዘለላ፡የአፍንጫሽም፡ሽቱ ፡እንደ፡እንኮይ፡ናቸው።

10፤ጕረሮሽ፡ለወዳጄ፡እየጣፈጠ፡እንደሚገባ፥የተኙትን፡ከንፈሮች፡ይናገሩ፡ዘንድ፡እንደሚያደርግ፥እንደ፡ማለ ፊያ፡የወይን፡ጠጅ፡ነው።

11፤እኔ፡የውዴ፡ነኝ፥የርሱም፡ምኞት፡ወደ፡እኔ፡ነው።

12፤ውዴ፡ሆይ፥ና፥ወደ፡መስክ፡እንውጣ፡በመንደሮችም፡እንደር።

13፤ወደወይኑ፡ቦታ፡ማልደን፡እንሂድ፤ወይኑ፡አብቦ፡አበባውም፡ፍሬ፡አንዠርጎ፡ሮማኑም፡አፍርቶ፡እንደ፡ኾነ ፡እንይ፤በዚያ፡ውዴን፡እሰጥኻለኹ።
14፤ትርንጎዎች፡መዐዛን፡ሰጡ፤መልካሞች፡ፍሬዎች፡ዅሉ፥አሮጌው፡ከዐዲሱ፡ጋራ፥በደጃችን፡አሉ፤ውዴ፡ሆይ፥ዅሉ ን፡ለአንተ፡ጠበቅኹልኽ።
__________________ማሕልየ፡መሓልይ፡ዘሰሎሞን፥ምዕራፍ፡8።_________________
ምዕራፍ፡8።
1፤አንተ፡የእናቴን፡ጡት፡እንደ፡ጠባ፡እንደ፡ወንድሜ፡ምነው፡በኾንኽ! በሜዳ፡ባገኘኹኽ፡ጊዜ፡በሳምኹኽ፥ማንም፡ባልናቀኝም፡ነበር።
2፤መርቼ፡ወደእናቴ፡ቤት፡ባገባኹኽ፥በዚያም፡አንተ፡ባስተማርከኝ፤እኔም፡ከመልካሙ፡ወይን፡ጠጅ፡ከሮማኔም፡ው ሃ፡ባጠጣኹኽ፡ነበር።
3፤ግራው፡ከራሴ፡በታች፡በኾነች፡ቀኙም፡ባቀፈችኝ፡ነበር።
4፤እናንተ፡የኢየሩሳሌም፡ቈነዦዥት፡ሆይ፥ርሱ፡እስኪፈልግ፡ድረስ፡ፍቅርን፡እንዳታስነሡት፡እንዳታነሣሡትም፡ አምላችኋለኹ።
5፤በውዷ፡ላይ፡ተደግፋ፡ከምድረ፡በዳ፡የምትወጣ፡ይህች፡ማን፡ናት፤ከእንኮይ፡በታች፡አስነሣኹኽ፤በዚያ፡እናት ኽ፡ወለደችኽ፥በዚያም፡ወላጅ፡እናትኽ አማጠችኽ።
6፤እንደ፡ማኅተም፡በልብኽ፥እንደ፡ማኅተም፡በክንድኽ፡አኑረኝ፤ፍቅር፡እንደ፡ሞት፡የበረታች፡ናትና፥ቅንአትም ፡እንደ፡ሲኦል፡የጨከነች፡ናትና።ፍንጣሪ እንደ፡እሳት፡ፍንጣሪ፥እንደእግዚአብሔር፡ነበልባል፡ነው።
7፤ብዙ፡ውሃ፡ፍቅርን፡ያጠፋት፡ዘንድ፡አይችልም፥ፈሳሾችም፡አያሰጥሟትም፤ሰው፡የቤቱን፡ሀብት፡ዅሉ፡ስለ፡ፍቅ ር፡ቢሰጥ፡ፈጽሞ፡ይንቁታል።
8፤እኛ፡ጡት፡የሌላት፡ታናሽ፡እኅት፡አለችን፤ስለ፡ርሷ፡በሚናገሩባት፡ቀን፡ለእኅታችን፡ምን፡እናድርግላት፤
9፤ርሷ፡ቅጥር፡ብትኾን፡የብር፡ግንብ፡በላይዋ፡እንሠራለን፤ደጅም፡ብትኾን፡በዝግባ፡ሳንቃ፡እንከቧታለን።
10፤እኔ፡ቅጥር፡ነኝ፡ጡቶቼም፡እንደ፡ግንብ፡ናቸው፤በዚያን፡ጊዜ፡በፊቱ፡ሰላምን፡እንደምታገኝ፡ኾንኹ።
11፤ለሰሎሞን፡በብኤላሞን፡የወይን፡ቦታ፡ነበረው፤የወይኑን፡ቦታ፡ለጠባቂዎች፡አከራየው፤ሰው፡ዅሉ፡ለፍሬው፡ ሺሕ፡ብር፡ያመጣለት፡ነበር።
12፤ለእኔ፡ያለኝ፡የወይን፡ቦታ፡በፊቴ፡ነው፤ሰሎሞን፡ሆይ፥ሺሑ፡ለአንተ፥ኹለት፡መቶውም፡ፍሬውን፡ለሚጠብቁ፡ ይኾናል።
13፤በገነቱ፡የምትቀመጪ፡ሆይ፥ባልንጀራዎች፡የአንቺን፡ቃል፡ያደምጣሉ፤ቃልሽን፡አሰሚኝ።
14፤ውዴ፡ሆይ፥ፍጠን፤በቅመም፡ተራራ፡ላይ፡ሚዳቋን፡ወይም፡የዋላን፡እንቦሳ፡ምሰል፡፡

# ትንቢተ ፡ ኢሳይያስ ።

(ክለሳ.1.20020507)

## ትንቢተ ፡ ኢሳይያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 1 ።

ምዕራፍ ፡ 1 ።

1 ፤ በይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ በዖዝያንና ፡ በኢዮአታም ፡ በአካዝና ፡ በሕዝቅያስ ፡ ዘመን ፡ ስለ ፡ ይሁዳና ፡ ስለ ፡ ኢየሩሳሌም ፡
ያየው ፡ የዓሞጽ ፡ ልጅ ፡ የኢሳይያስ ፡ ራእይ ።

2 ፤ እግዚአብሔር ፡ ተናግሯልና ፥ ሰማያት ፡ ስሙ ፥ ምድርም ፡ አድምጪ ፤ ልጆችን ፡ ወለድኍ ፡
አሳደግኍም ፥ እነርሱም ፡ ዐመፁብኝ ።

3 ፤ በሬ ፡ የገዛውን ፡ አህያም ፡ የጌታውን ፡ ጋጣ ፡ ዐወቀ ፤ እስራኤል ፡ ግን ፡ አላወቀም ፥ ሕዝቤም ፡ አላስተዋለም ።

4 ፤ ኀጢአተኛ ፡ ወገንና ፡ በደል ፡ የተሞላበት ፡ ሕዝብ ፥ የክፉዎች ፡ ዘር ፥ ርኵሰትን ፡ የምታደርጉ ፡ ልጆች ፡
ሆይ ፥ ወዮላችኍ! እግዚአብሔርን ፡ ትተዋል ፡ የእስራኤልንም ፡ ቅዱስ ፡ አቃለዋል ፥ ወደ ፡ ኋላቸውም ፡ እየኼዱ ፡
ተለይተዋል ።

5 ፤ ደግሞስ ፡ ዐመፃ ፡ እየጨመራችኍ ፡ ለምን ፡ ገና ፡ ትቀሰፋላችኍ ፧ ራስ ፡ ኹሉ ፡ ለሕመም ፥ ልብም ፡ ኹሉ ፡
ለድካም ፡ ኾኗል ።

6 ፤ ከእግር ፡ ጫማ ፡ አንሥቶ ፡ እስከ ፡ ራስ ፡ ድረስ ፡ ጤና ፡ የለውም ፤ ቍስልና ፡ ዕበጥ ፡ የሚመግልም ፡
ነው ፤ አልፈረጠም ፥ አልተጠገነም ፥ በዘይትም ፡ አልለዘበም ።

7 ፤ ምድራችኍ ፡ ባድማ ፡ ናት ፤ ከተማዎቻችኍ ፡ በእሳት ፡ ተቃጠሉ ፤ ዕርሻችኍንም ፡ በፊታችኍ ፡ ሌላዎች ፡
ይበሉታል ፤ ባዕድ ፡ እንዳፈረሳት ፡ ምድር ፡ ባድማ ፡ ኾነች ።

8 ፤ የጽዮንም ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ በወይን ፡ ቦታ ፡ እንዳለ ፡ ዳስ ፥ በዱባ ፡ አትክልትም ፡ እንዳለ ፡ ጐጆ ፥ አንደ ፡ ተከበበችም ፡
ከተማ ፡ ኾና ፡ ቀረች ።

9 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዘርን ፡ ባያስቀርልን ፡ ኖሮ ፥ እንደ ፡ ሰዶም ፡ በኾንን ፡ እንደ ፡ ገሞራም ፡ በመሰልን ፡
ነበር ።

10 ፤ እናንተ ፡ የሰዶም ፡ አለቃዎች ፡ ሆይ ፥ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስሙ ፤ እናንተ ፡ የገሞራ ፡ ሕዝብ ፡
ሆይ ፥ የአምላካችንን ፡ ሕግ ፡ አድምጡ ።

11 ፤ የመሥዋዕታችኍ ፡ ብዛት ፡ ለእኔ ፡ ምን ፡ ይጠቅመኛል ፧ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ የሚቃጠለውን ፡ የአውራ ፡ በግ ፡
መሥዋዕትንና ፡ የፍሪዳን ፡ ስብ ፡ ጠግቤያለኍ ፤ የበሬና ፡ የበግ ፡ ጠቦት ፡ የአውራ ፡ ፍየልም ፡ ደም ፡ ደስ ፡ አያሠኘኝም ።

12 ፤ በእኔ ፡ ፊት ፡ ልትታዩ ፡ ብትመጡ ፡ ይህን ፡ የመቅደሴን ፡ አደባባይ ፡ መርገጣችኍን ፡ ከእጃችኍ ፡ የሚሻ ፡ ማን ፡
ነው ፧

13 ፤ ምናምንቴውን ፡ ቍርባን ፡ ጨምራችኍ ፡ አታምጡ ፤ ዕጣን ፡ በእኔ ፡ ዘንድ ፡ አጸያፊ ፡ ነው ፤ መባቻችኍንና ፡
ሰንበታችኍን ፡ በጉባኤ ፡ መሰብሰባችኍን ፡ አልወድም ፤ በደልንም ፡ የተቀደሰውንም ፡ ጉባኤ ፡ አልታገሥም ።

14 ፤ መባቻችኍንና ፡ በዓላቶቻችኍን ፡ ነፍሴ ፡ ጠልታለች ፤ ሸክም ፡ ኾነውብኛል ፥ ልታገሣቸውም ፡ ደክሜያለኍ ።

15 ፤ እጃችኍንም ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ብትዘረጉ ፡ ዐይኔን ፡ ከእናንተ ፡ እሰውራለኍ ፥ ልመናንም ፡ ብታበዙ ፡
አልሰማችኍም ፤ እጆቻችኍ ፡ ደም ፡ ተሞልተዋል ።

16 ፤ ታጠቡ ፡ ሰውነታችኍንም ፡ አንጹ ፤ የሥራችኍን ፡ ክፋት ፡ ከዐይኔ ፡ ፊት ፡ አስወግዱ ፤ ክፉ ፡ ማድረግን ፡ ተዉ ፥

17 ፤ መልካም ፡ መሥራትን ፡ ተማሩ ፥ ፍርድን ፡ ፈልጉ ፥ የተገፋውን ፡ አድኑ ፥ ለድኻ ፡ አደጉ ፡ ፍረዱለት ፡ ስለ ፡

መበለቲቱም ፡ ተሟገቱ ።

18 ፤ ኑና ፡ እንዋቀስ ፡ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ ኀጢአታችኹ ፡ እንደ ፡ ዐለላ ፡ ብትኾን ፡ እንደ ፡ ዐመዳይ ፡
ትነጻለች ፤ እንደ ፡ ደምም ፡ ብትቀላ ፡ እንደ ፡ ባዘቶ ፡ ትጠራለች ።

19 ፤ ዕሺ ፡ ብትሉ ፡ ለኔም ፡ ብትታዘዙ ፥ የምድርን ፡ በረከት ፡ ትበላላችኹ ፤

20 ፤ እምቢ ፡ ብትሉ ፡ ግን ፡ ብታምፁም ፥ ሰይፍ ፡ ይበላችኋል ፤ የእግዚአብሔር ፡ አፍ ፡ ይህን ፡ ተናግሯልና ፦

21 ፤ ፍርድ ፡ ሞልቶባት ፡ የነበረው ፡ የታመነችዪቱ ፡ ከተማ ፡ እንዴት ፡ ጋለሞታ ፡ ኾነች! ጽድቅ ፡ ዐድሮባት ፡
ነበር ፥ አኹን ፡ ግን ፡ ገዳዮች ፡ አሉባት ።

22 ፤ ብርሽ ፡ ወደ ፡ ዝገት ፡ ተለወጠ ፤ የወይን ፡ ጠጅሽ ፡ ከውሃ ፡ ጋራ ፡ ተደባለቀ ።

23 ፤ አለቃዎችሽ ፡ ዐመፀኛዎችና ፡ የሌቦች ፡ ባልንጀራዎች ፡ ኾኑ ፤ ኹሉ ፡ ጉቦ ፡ ይወዳሉ ፥ ዋጋም ፡ ለማግኘት ፡
ይሮጣሉ ፤ ለድኻ ፡ አደጉ ፡ አይፈርዱም ፥ የመበለቲቱም ፡ሙግት ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ አይደርስም ።

24 ፤ ስለዚህ ፥ የእስራኤል ፡ ኀያል ፥ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ በጠላቶቼ ፡ ላይ ፡ ቍጣዬን ፡
እፈጽማለኹ ፥ የሚቋቋሙኝንም ፡ እበቀላለኹ ።

25 ፤ እጄንም ፡ ባንቺ ፡ ላይ ፡ አመጣለኹ ፥ ዝገትሽንም ፡ በጣም ፡ አነጻለኹ ፥ ቈርቈሮሽንም ፡ ኹሉ ፡ አወጣለኹ ፤

26 ፤ ፈራጆችሽንም ፡ እንደ ፡ ቀድሞ ፡ አማካሪዎችሽንም ፡ እንደ ፡ መዠመሪያው ፡ ጊዜ ፡ መልሼ ፡ አስነሣለኹ ፤ ከዚያም ፡
በኋላ ፡ የጽድቅ ፡ ከተማ ፡ የታመነችም ፡ ከተማ ፡ ተብለሽ ፡ ትጠሪያለሽ ።

27 ፤ ጽዮን ፡ በፍርድ ፡ ከርሷም ፡ የሚመለሱ ፡ በጽድቅ ፡ ይድናሉ ።

28 ፤ በደለኛዎችና ፡ ኀጢአተኛዎች ፡ ግን ፡ በአንድነት ፡ ይሰበራሉ ፥ እግዚአብሔርንም ፡ የሚተዉ ፡ ይጠፋሉ ።

29 ፤ በወደዳችኋት ፡ የአድባር ፡ ዛፍ ፡ ታፍራላችኹና ፥ ስለ ፡ መረጣችኋትም ፡ አትክልት ፡ ዕፍረት ፡ ይይዛችኋልና ፤

30 ፤ ቅጠሏ ፡ እንደ ፡ ረገፈ ፡ ዛፍ ፥ ውሃም ፡ እንደሌለባት ፡ አትክልት ፡ ትኾናላችኹና ።

31 ፤ ኀይለኛውም ፡ እንደ ፡ ተልባ ፡ ጭረት ፥ ሥራውም ፡ እንደ ፡ ጠለሸት ፡ ይኾናል ፤ ዐብረውም ፡ ይቃጠላሉ ፡
እነርሱንም ፡ የሚያጠፋ ፡ የለም ።

ትንቢተ ፡ ኢሳይያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 2 ።

ምዕራፍ ፡ 2 ።

1 ፤ የዓሞጽ ፡ ልጅ ፡ ኢሳይያስ ፡ ስለ ፡ ይሁዳና ፡ ስለ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ያየው ፡ ቃል ።

2 ፤ በዘመኑም ፡ ፍጻሜ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ተራራ ፡ በተራራዎች ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ጸንቶ ፡ ይቆማል ፥ ከኰረብታዎችም ፡
በላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ፥ አሕዛብም ፡ ኹሉ ፡ ወደ ፡ ርሱ ፡ ይሰበሰባሉ ።

3 ፤ ሕግ ፡ ከጽዮን ፡ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ይወጣልና ፥ ብዙዎች ፡ አሕዛብ ፡
ኼደው ፦ ኑ ፥ ወደእግዚአብሔር ፡ ተራራ ፥ ወደያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ ቤት ፡ እንውጣ ፤ ርሱም ፡ መንገዱን ፡
ያስተምረናል ፥ በጐዳናውም ፡ እንኼዳለን ፡ ይላሉ ።

4 ፤ በአሕዛብም ፡ መካከል ፡ ይፈርዳል ፥ በብዙ ፡ አሕዛብም ፡ ላይ ፡ ይበይናል ፤ ሰይፋቸውንም ፡ ማረሻ ፡ ጦራቸውንም ፡
ማጭድ ፡ ለማድረግ ፡ ይቀጠቅጣሉ ፤ ሕዝብም ፡ በሕዝብ ፡ ላይ ፡ ሰይፍ ፡ አያነሣም ፥ ሰልፍም ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡
አይማሩም ።

5 ፤ እናንተ ፡ የያዕቆብ ፡ ቤት ፡ ሆይ ፥ ኑ ፥ በእግዚአብሔር ፡ ብርሃን ፡ እንኺድ ።

6 ፤ ሕዝብኽን ፡ የያዕቆብን ፡ ቤት ፡ ትተኻልና ፤ ይኸውም ፡ የምሥራቅን ፡ ሰዎች ፡ ዐመል ፡ ስለ ፡ ተሞሉ ፥ እንደ ፡
ፍልስጥኤማውያንም ፡ ሟርተኛዎች ፡ ስለ ፡ ኾኑ ፥ ከባዕድ ፡ ልጆችም ፡ ጋራ ፡ ስለ ፡ ተባበሩ ፡ ነው ።

7 ፤ ምድራቸው ፡ በብርና ፡ በወርቅ ፡ ተሞልታለች ፥ ለመዛግብቶቻቸውም ፡ ፍጻሜ ፡ የለውም ፤ ምድራቸውም ፡ ደግሞ ፡
በፈረሶች ፡ ተሞልታለች ፥ ለሠረገላዎቻቸውም ፡ ፍጻሜ ፡ የለውም ።

8 ፤ ምድራቸው ፡ ደግሞ ፡ በጣዖታት ፡ ተሞልታለች ፤ ጣቶቻቸውም ፡ ላደረጉት ፡ ለእጃቸው ፡ ሥራ ፡ ይሰግዳሉ ።

9 ፤ ታናሹም ፡ ሰው ፡ ዝቅ ፡ ብሏል ፥ ጨዋውም ፡ ተዋርዷል ፤ ኀጢአታቸውንም ፡ ይቅር ፡ አትበላቸው ።

10 ፤ ከእግዚአብሔር ፡ ማስደንገጥና ፡ ከግርማው ፡ ክብር ፡ የተነሣ ፡ ወደድንጋይ ፡ ዋሻ ፡ ግባ ፥ በመሬትም ፡ ውስጥ ፡ ተሸሸግ ።

11 ፤ ከፍ ፡ ያለችውም ፡ የሰው ፡ ዐይን ፡ ትዋረዳለች ፥ የሰዎችም ፡ ኵራት ፡ ትወድቃለች ፥ በዚያም ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ ብቻውን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ።

12 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቀን ፡ በትዕቢተኛውና ፡ በኵራተኛው ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ባለውም ፡ ላይ ፡ ይኾናል ፥ ርሱም ፡ ይዋረዳል ፤

13 ፤ ደግሞም ፡ በረዥሙ ፡ ከፍ ፡ ባለው ፡ በሊባኖስ ፡ ዝግባ ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፥ በባሳንም ፡ ዛፍ ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፥

14 ፤ በረዥሙም ፡ ተራራ ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፥ ከፍ ፡ ባለውም ፡ ኰረብታ ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፥

15 ፤ በረዥሙም ፡ ግንብ ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፥ በተመሸገውም ፡ ቅጥር ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፥

16 ፤ በተርሴስም ፡ መርከብ ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፥ በሚያማምሩ ፡ ጣዖታትም ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፡ ይኾናል ።

17 ፤ ሰውም ፡ ኹሉ ፡ ይዋረዳል ፥ የሰውም ፡ ኵራት ፡ ይወድቃል ፥ በዚያም ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ ብቻ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ።

18 ፤ ጣዖቶቻቸውም ፡ ኹሉ ፡ ፈጽመው ፡ ይጠፋሉ ።

19 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ምድርን ፡ ያናውጥ ፡ ዘንድ ፡ በተነሣ ፡ ጊዜ ፥ ሰዎች ፡ ከማስደንገጡና ፡ ከግርማው ፡ ክብሩ ፡ የተነሣ ፥ ወደድንጋይ ፡ ዋሻና ፡ ወደምድር ፡ ንቃቃት ፡ ውስጥ ፡ ይገባሉ ።

20 ፤ በዚያን ፡ ቀን ፡ ሰው ፡ ይሰግድላቸው ፡ ዘንድ ፡ ያበጃቸውን ፡ የብሩንና ፡ የወርቁን ፡ ጣዖቶቹን ፡ ለፍልፈልና ፡ ለሌሊት ፡ ወፍ ፡ ይጥላል ።

21 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ምድርን ፡ ያናውጥ ፡ ዘንድ ፡ በተነሣ ፡ ጊዜ ፡ ከማስደንገጡና ፡ ከግርማው ፡ ክብር ፡ የተነሣ ፡ ወደድንጋይ ፡ ዋሻና ፡ ወደተሰነጠቁ ፡ አለቶች ፡ ውስጥ ፡ ይገባሉ ።

22 ፤ እስትንፋሱ ፡ በአፍንጫው ፡ ውስጥ ፡ ያለበትን ፡ ሰው ፡ ተዉት ፤ ርሱ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ይቈጠራል ፧

## ትንቢተ ፡ ኢሳይያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 3 ።

ምዕራፍ ፡ 3 ።

1 ፤ እንሆ ፥ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከኢየሩሳሌምና ፡ ከይሁዳ ፡ ድጋፍንና ፡ ብርታትን ፥ የእንጀራን ፡ ድጋፍ ፡ ኹሉ ፡ የውሃውንም ፡ ድጋፍ ፡ ኹሉ ፥

2 ፤ ኀያሉንም ፥ ተዋጊውንም ፥ ፈራጁንም ፥ ነቢዩንም ፥ ሟርተኛውንም ፥

3 ፤ ሸማግሌውንም ፥ የዐምሳ ፡ አለቃውንም ፥ ከበርቴውንም ፥ አማካሪውንም ፥ ብልኁንም ፡ ሠራተኛ ፥ አስማት ፡ ዐዋቂውንም ፡ ይነቅላል ።

4 ፤ አለቃዎቻቸው ፡ እንዲኾኑ ፡ ብላቴናዎችን ፡ አስነሣባቸዋለኹ ፥ ሕፃናትም ፡ ይገዟቸዋል ።

5 ፤ ሕዝቡም ፥ ሰው ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ ሰውም ፡ በባልንጀራው ፡ ላይ ፥ ይገፋፋል ፤ ብላቴናውም ፡ በሽማግሌው ፡ ላይ ፡ የተጠቃውም ፡ በከበርቴው ፡ ላይ ፡ ይኰራል ።

6 ፤ ሰውም ፡ በአባቱ ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ ወንድሙን ፡ ይዞ ፦ አንተ ፡ ልብስ ፡ አለኽ ፡ አለቃም ፡ ኹንልን ፡ ይህችም ፡ ባድማ ፡ ከእጅኽ ፡ በታች ፡ ትኹን ፡ ሲለው ፥

7 ፤ በዚያ ፡ ቀን ፡ ድምፁን ፡ ከፍ ፡ አድርጎ ፦ እኔ ፡ በቤቴ ፡ ውስጥ ፡ እንጀራ ፡ ወይም ፡ ልብስ ፡ የለኝምና ፡ ባለመድኀኒት ፡ አልኾንም ፤ በሕዝቡም ፡ ላይ ፡ አለቃ ፡ አታደርጉኝም ፡ ይላል ።

8 ፤ የክብሩን ፡ ዐይን ፡ ያስቈጡ ፡ ዘንድ ፡ ምላሳቸውና ፡ ሥራቸው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ ነውና ፥ ኢየሩሳሌም ፡ ተፈታች ፥ ይሁዳም ፡ ወደቀ ።

9 ፤ የፊታቸውም ፡ ዕፍረት ፡ ይመሰክርባቸዋል ፤ እንደ ፡ ሰዶምም ፡ ኀጢአታቸውን ፡ ያወራሉ ፥ አይሰውሯትም ። በራሳቸው ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡ ሠርተዋልና ፥ ለነፍሳቸው ፡ ወዮ!

10 ፤ የሥራቸውን ፡ ፍሬ ፡ ይበላሉና ፡ ጻድቁን ፦ መልካም ፡ ይኾንልኻል ፡ በሉት ።

11 ፤ እንደ ፡ እጁ ፡ ሥራ ፡ ፍዳው ፡ ይደረግበታልና ፥ ለበደለኛ ፡ ወዮ! ክፉም ፡ ደርሶበታል ።

12 ፤ ሕዝቤንስ ፡ አስገባሪዎቻቸው ፡ ይገፏቸዋል ፥ አስጨናቂዎችም ፡ ይሠለጥኑባቸዋል ። ሕዝቤ ፡ ሆይ ፥ የመሯችኹ ፡ ያስቷችኻል ፡ የምትኼዱበትንም ፡ መንገድ ፡ ያጠፋሉ ።

13 ፤ እግዚአብሔር ፡ ለፍርድ ፡ ተነሥቷል ፡ በሕዝቡም ፡ ላይ ፡ ሊፈርድ ፡ ቆሟል ።

14 ፤ እግዚአብሔር ፡ ከሕዝቡ ፡ ሽማግሌዎችና ፡ ከአለቃዎቻቸው ፡ ጋራ ፡ ይፋረዳል ፤ የወይኑን ፡ ቦታ ፡ የጨረሳችኹ ፡ እናንተ ፡ ናችኹ ፤ ከድኻዎች ፡ የበዘበዛችኹት ፡ በቤታችኹ ፡ አለ ፤

15 ፤ ሕዝቤንም ፡ ለምን ፡ ታደቋቸዋላችኹ ፧ የድኻዎችንስ ፡ ፊት ፡ ለምን ፡ ትፈጩላችኹ ፧ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

16 ፤ ደግሞም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ አለ ፦ የጽዮን ፡ ቈነጃጅት ፡ ኰርተዋልና ፥ ዐንገታቸውንም ፡ እያሰገጉ ፡ በዐይናቸውም ፡ እያጣቀሱ ፥ ፈንጠርም ፡ እያሉ ፥ በእግራቸውም ፡ እያቃጨሉ ፡ ይኼዳሉና ፥

17 ፤ ስለዚህ ፥ ጌታ ፡ የጽዮንን ፡ ቈነጃጅት ፡ ዐናት ፡ በቡሓነት ፡ ይመታል ፥ እግዚአብሔርም ፡ ኀፍረተ ፡ ሥጋቸውን ፡ ይገልጣል ።

18 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ ጌታ ፡ የእግር ፡ አልቦውን ፡ ክብር ፥ መርበብንም ፥ ጨረቃ ፡ የሚመስለውንም ፡ ጌጥ ፥ የጕሮ ፡ እንጥልጥሉንም ፥

19 ፤ አንባሩንም ፥ መሸፈኛውንም ፥ ቀጸላውንም ፥

20 ፤ ሰንሰለቱንም ፥ መቀነቱንም ፥ የሽቱውንም ፡ ዕቃ ፥

21 ፤ ዐሸን ፡ ክታቡንም ፥ የእጅና ፡ የአፍንጫ ፡ ቀለበቱንም ፥

22 ፤ የዓመት ፡ በዓልንም ፡ ልብስ ፥ መጐናጸፊያውንም ፥ ልግም ፡ በገላውንም ፥ ከረጢቱንም ፥

23 ፤ መስተዋቱንም ፥ ከጥሩ ፡ በፍታ ፡ የተሠራውንም ፡ ልብስ ፥ ራስ ፡ ማሰሪያውንም ፥ ዐይነ ፡ ርግቡንም ፡ ያስወግዳል ።

24 ፤ እንዲህም ፡ ይኾናል ፤ በሽቱ ፡ ፋንታ ፡ ግማት ፥ በመታጠቂያውም ፡ ፋንታ ፡ ገመድ ፥ ጠጕርንም ፡ በመንቀስ ፡ ፋንታ ፡ ቡሓነት ፥ በመጐናጸፊያ ፡ ፋንታ ፡ ማቅ ፥ በውበትም ፡ ፋንታ ፡ ጠባሳ ፡ ይኾናል ።

25 ፤ ጕልማሳዎችሽ ፡ በሰይፍ ፥ ኀያላንሽም ፡ በውጊያ ፡ ይወድቃሉ ።

26 ፤ በሮቿ ፡ ያዝናሉ ፡ ያለቅሱማል ፤ ርሷም ፡ ብቻዋን ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ትቀመጣለች ።

ትንቢተ ፡ ኢሳይያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 4 ።

ምዕራፍ ፡ 4 ።

1 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ ሰባት ፡ ሴቶች ። የገዛ ፡ እንጀራችንን ፡ እንበላለን ፡ የገዛ ፡ ልብሳችንንም ፡ እንለብሳለን ፤ ስምኽ ፡ ብቻ ፡ በእኛ ፡ ላይ ፡ ይጠራ ፥ መሰደባችንንም ፡ አርቅ ፡ ብለው ፡ አንዱን ፡ ወንድ ፡ ይይዙታል ።

2 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቍጥቋጥ ፡ ለጌጥና ፡ ለክብር ፡ ይኾናል ፥ ከእስራኤልም ፡ ወገን ፡ ላመለጡ ፡ ሰዎች ፡ የምድሪቱን ፡ ፍሬ ፡ ለትምክሕትና ፡ ለውበት ፡ ይኾናል ።

3 ፤ 4 ፤ ጌታም ፡ የጽዮንን ፡ ቈነጃጅት ፡ እድፍ ፡ ባጠበ ፡ ጊዜ ፥ የኢየሩሳሌምንም ፡ ደም ፡ በፍርድ ፡ መንፈስና ፡ በሚያቃጥል ፡ መንፈስ ፡ ከመካከሏ ፡ ባነጻ ፡ ጊዜ ፥ በጽዮን ፡ የቀረ ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ የተረፈ ፥ በኢየሩሳሌም ፡ ለሕይወት ፡ የተጻፈ ፡ ኹሉ ፥ ቅዱስ ፡ ይባላል ።

5 ፤ እግዚአብሔርም ፡ በጽዮን ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ባለ ፡ ማደሪያ ፡ ዅሉ ፡ በጉባኤያቸውም ፡ ላይ ፡ በቀን ፡ ዳመናንና ፡ ጢስን ፡ በሌሊትም ፡ የሚቃጠለውን ፡ የእሳት ፡ ብርሃን ፡ ይፈጥራል ፤ በክብርም ፡ ዅሉ ፡ ላይ ፡ መጋረጃ ፡ ይኾናል ።

6 ፤ በቀን ፡ ከሙቀት ፡ ለጥላ ፥ ከዐውሎ ፡ ነፋስና ፡ ከዝናብም ፡ ለመጠጊያና ፡ ለመሸሸጊያ ፡ ጐጆ ፡ ይኾናል ።

__________________ትንቢተ ፡ ኢሳይያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 5 ። __________________

ምዕራፍ ፡ 5 ።

1 ፤ አኹን ፡ ስለ ፡ ወዳጄና ፡ ስለወይን ፡ ቦታው ፡ ለወዳጄ ፡ ቅኔ ፡ እቀኛለኹ ። ለወዳጄ ፡ በፍሬያማው ፡ ኰረብታ ፡ ላይ ፡ የወይን ፡ ቦታ ፡ ነበረው ።

2 ፤ በዙሪያው ፡ ቈፈረ ፥ ድንጋዮችንም ፡ ለቅሞ ፡ አወጣ ፥ ምርጥ ፡ የኾነውንም ፡ ዐረግ ፡ ተከለበት ፥ በመካከሉም ፡ ግንብ ፡ ሠራ ፥ ደግሞም ፡ የመጥመቂያ ፡ ጕድጓድ ፡ ማሰበት ፤ ወይንንም ፡ ያፈራ ፡ ዘንድ ፡ ተማመነ ፥ ዳሩ ፡ ግን ፡ ሖምጣጣ ፡ ፍሬ ፡ አፈራ ።

3 ፤ አኹንም ፡ እናንተ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የምትኖሩ ፡ የይሁዳ ፡ ሰዎች ፡ ሆይ ፥ በእኔና ፡ በወይኑ ፡ ቦታዬ ፡ መካከል ፡ እስኪ ፡ ፍረዱ ።

4 ፤ ለወይኔ ፡ ያላደረግኹለት ፥ ከዚህ ፡ ሌላ ፡ አደርግለት ፡ ዘንድ ፡ የሚገባኝ ፡ ምንድር ፡ ነው ፡ ወይንን ፡ ያፈራል ፡ ብዬ ፡ ስተማመን ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ሖምጣጣ ፡ ፍሬ ፡ አፈራ ፡

5 ፤ አኹንም ፡ በወይኔ ፡ ላይ ፡ የማደርገውን ፡ እነግራችኋለኹ ፤ ዐጥሩን ፡ እነቅላለኹ ፥ ለማሰማሪያም ፡ ይኾናል ፤ ቅጥሩንም ፡ አፈርሳለኹ ፥ ለመራገጫም ፡ ይኾናል ።

6 ፤ ባድማ ፡ አደርገዋለኹ ፤ አይቈረጥም ፥ አይኰተኰትም ፤ ኵርንችትና ፡ ሾኽ ፡ ይበቅልበታል ፤ ዝናብንም ፡ እንዳያዘንቡበት ፡ ዳመናዎችን ፡ አዛለኹ ።

7 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ወይን ፡ ቦታ ፡ ርሱ ፡ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ነው ፥ የደስታውም ፡ አትክልት ፡ የይሁዳ ፡ ሰዎች ፡ ናቸው ፤ ፍርድን ፡ ተስፋ ፡ ያደርግ ፡ ነበር ፥ እንሆም ፡ ደም ፡ ማፍሰስ ፡ ኾነ ፤ ጽድቅንም ፡ ይተማመን ፡ ነበር ፥ እንሆም ፥ ጩኸት ፡ ኾነ ።

8 ፤ ስፍራ ፡ እስከማይቀር ፡ ድረስ ፡ እናንተም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ብቻችኹን ፡ እስክትቀመጡ ፡ ድረስ ፥ ቤትን ፡ ከቤት ፡ ጋራ ፡ ለሚያያይዙ ፡ ዕርሻንም ፡ ከዕርሻ ፡ ጋራ ፡ ለሚያቀራርቡ ፡ ወዮላቸው!

9 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ በጆሮዬ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— በእውነት ፡ ብዙ ፡ ታላቅና ፡ መልካም ፡ ቤት ፡ ባድማ ፡ ይኾናል ፥ የሚቀመጥበትም ፡ አይገኝም ።

10 ፤ ከወይኑ ፡ ቦታ ፡ ዐሥር ፡ ጥማድ ፡ በሬ ፡ ካረሰው ፡ አንድ ፡ የባዶስ ፡ መስፈሪያ ፡ ብቻ ፡ ይወጣል ፤ አንድ ፡ የቆሮስ ፡ መስፈሪያ ፡ ዘር ፡ አንድ ፡ የኢፍ ፡ መስፈሪያ ፡ ብቻ ፡ ይሰጣል ።

11 ፤ ስካርን ፡ ለመከተል ፡ በጧት ፡ ለሚማልዱ ፥ የወይን ፡ ጠጅም ፡ እስኪያቃጥላቸው ፡ እስከ ፡ ሌሊት ፡ ድረስ ፡ ለሚዘገዩ ፡ ወዮላቸው!

12 ፤ መሰንቆና ፡ በገና ፡ ከበሮና ፡ እንቢልታም ፡ የወይን ፡ ጠጅም ፡ በግብዣቸው ፡ አለ ፤ የእግዚአብሔርን ፡ ሥራ ፡ ግን ፡ አልተመለከቱም ፥ እጁም ፡ ያደረገችውን ፡ አላስተዋሉም ።

13 ፤ ስለዚህ ፥ ሕዝቤ ፡ ወደ ፡ ምርኮ ፡ ኼዱ ፥ ጌታን ፡ አላወቁትምና ፤ ከበርቴዎቻቸውም ፡ ተራቡ ፥ ሕዝባቸውም ፡ ተጠሙ ።

14 ፤ ሲኦልም ፡ ሆዷን ፡ አስፍታለች ፥ አፏንም ፡ ያለልክ ፡ ከፍታለች ፤ ከበርቴዎቻቸውና ፡ ዐዛውንቶቻቸው ፡ ባለጠጋዎቻቸውም ፡ ደስተኛዎቻቸውም ፡ ወደ ፡ ርሷ ፡ ይወርዳሉ ።

15 ፤ ሰውም ፡ ይጐሰቈላል ፥ ሰውም ፡ ይዋረዳል ፥ የትዕቢተኛዎችም ፡ ዐይን ፡ ትዋረዳለች ፤

16 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ በፍርድ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብሏል ፥ ቅዱሱም ፡ አምላክ ፡ በጽድቅ ፡ ተቀድሷል ።

17 ፤ የበግ ፡ ጠቦቶች ፡ በማሰማሪያቸው ፡ ውስጥ ፡ ይሰማራሉ ፥ እንግዳዎችም ፡ የሰቡትን ፡ ባድማ ፡ ይበላሉ ።

18 ፤ በደልን ፡ በምናምንቴ ፡ ገመድ ፥ ኀጢአትንም ፡ በሠረገላ ፡ ማሰሪያ ፡ ወደ ፡ ራሳቸው ፡ ለሚስቡ ፦ እናዩ ፡ ዘንድ ፡ ይቸኵል ፥

19 ፤ ሥራውንም ፡ ያፋጥን ፤ እናውቃትም ፡ ዘንድ ፡ የእስራኤል ፡ ቅዱስ ፡ ምክር ፡ ትቅረብ ፥ ትምጣ ፡ ለሚሉ ፡ ወዮላቸው!

20 ፤ ክፉውን ፡ መልካም ፡ መልካሙን ፡ ክፉ ፡ ለሚሉ ፥ ጨለማውን ፡ ብርሃን ፡ ብርሃኑንም ፡ ጨለማ ፡ ለሚያደርጉ ፥ ጣፋጩን ፡ መራራ ፡ መራራውንም ፡ ጣፋጭ ፡ ለሚያደርጉ ፡ ወዮላቸው!

21 ፤ በዐይናቸው ፡ ጥበበኛዎች ፡ በነፍሳቸውም ፡ አስተዋዮች ፡ ለኾኑ ፡ ወዮላቸው!

22 ፤ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ለመጠጣት ፡ ኀያላን ፡ የሚያሰክረውንም ፡ ለማደባለቅ ፡ ጨካኞች ፡ ለኾኑ ፤

23 ፤ በደለኛውን ፡ ስለ ፡ ጉቦ ፡ ጻድቅ ፡ ለሚያደርጉ ፥ የጻድቁንም ፡ ጽድቅ ፡ ለሚያስወግዱበት ፡ ወዮላቸው!

24 ፤ ስለዚህ ፥ የእሳት ፡ ወላፈን ፡ ቃርሚያን ፡ እንደሚበላ ፥ እብቅም ፡ በነበልባል ፡ ውስጥ ፡ እንደሚጠፋ ፥ እንዲሁ ፡
የእነርሱ ፡ ሥር ፡ የበሰበሰ ፡ ይኾናል ፥ ቡቃያቸውም ፡ እንደ ፡ ትቢያ ፡ ይበናል ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡
ጥለዋልና ፥ የእስራኤልም ፡ ቅዱስ ፡ የተናገረውን ፡ ቃል ፡ አቃለዋልና ።

25 ፤ ስለዚህ ፥ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ ነዷል ፥ እጁንም ፡ በላያቸው ፡ ዘርግቶ ፡
መትቷቸዋል ፤ ተራራዎችም ፡ ተንቀጠቀጡ ፥ ሬሳቸውም ፡ በአደባባይ ፡ መካከል ፡ እንደ ፡ ጕድፍ ፡ ኾኗል ። በዚህም ፡
ኹሉ ፡ እንኳ ፡ ቍጣው ፡ አልተመለሰችም ፥ ነገር ፡ ግን ፥ እጁ ፡ ገና ፡ ተዘርግታ ፡ ትኖራለች ።

26 ፤ ለአሕዛብም ፡ በሩቅ ፡ ምልክትን ፡ ያቆማል ፥ ከምድርም ፡ ዳርቻ ፡ በፉጨት ፡ ይጠራቸዋል ፤ እንሆም ፥ እየተጣደፉ ፡ ፈጥነው ፡ ይመጣሉ ።

27 ፤ ደካማና ፡ ስንኩል ፡ የለባቸውም ፥ የሚያንቀላፋና ፡ የሚተኛም ፡ የለም ፤ የወገባቸውም ፡ መቀነት ፡ አይፈታም ፥ የጫማቸውም ፡ ማዘቢያ ፡ አይበጠስም ።

28 ፤ ፍላጻዎቻቸው ፡ ተስለዋል ፥ ቀስቶቻቸውም ፡ ኹሉ ፡ ተለጥጠዋል ፤ የፈረሶቻቸውም ፡ ኰቴ ፡ እንደ ፡ ቡላድ ፡ የሠረገላዎቻቸውም ፡ መንኰራኵር ፡ እንደ ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ ይቈጠራል ።

29 ፤ ጩኸታቸው ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ነው ፥ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ደቦሎችም ፡ ያገሣሉ ፤ ንጥቂያንም ፡ ይዘው ፡ ያገሣሉ ፥ ይወስዱትማል ፥ የሚያድንም ፡ የለም ።

30 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ እንደ ፡ ባሕር ፡ መትመም ፡ ይተምሙባቸዋል ፤ ወደ ፡ ምድርም ፡ ቢመለከቱ ፥ እንሆ ፥ ጨለማና ፡ መከራ ፡ አለ ፤ ብርሃንም ፡ በደመናዎቿ ፡ ውስጥ ፡ ጨልሟል ።

ትንቢተ ፡ ኢሳይያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 6 ።

ምዕራፍ ፡ 6 ።

1 ፤ ንጉሡ ፡ ዖዝያን ፡ በሞተበት ፡ ዓመት ፡ እግዚአብሔርን ፡ በረዥምና ፡ ከፍ ፡ ባለ ፡ ዙፋን ፡ ላይ ፡ ተቀምጦ ፡ አየኹት ፥ የልብሱም ፡ ዘርፍ ፡ መቅደሱን ፡ ሞልቶት ፡ ነበር ።

2 ፤ ሱራፌልም ፡ ከርሱ ፡ በላይ ፡ ቆመው ፡ ነበር ፥ ለያንዳንዱም ፡ ስድስት ፡ ክንፍ ፡ ነበረው ፤ በኹለት ፡ ክንፍ ፡ ፊቱን ፡ ይሸፍን ፡ ነበር ፥ በኹለቱም ፡ ክንፍ ፡ እግሮቹን ፡ ይሸፍን ፡ ነበር ፥ በኹለቱም ፡ ክንፍ ፡ ይበር ፡ ነበር ።

3 ፤ አንዱም ፡ ለአንዱ ፦ ቅዱስ ፥ ቅዱስ ፥ ቅዱስ ፥ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ ምድር ፡ ኹሉ ፡ ከክብሩ ፡ ተሞልታለች ፡ እያለ ፡ ይጮኽ ፡ ነበር ።

4 ፤ የመድረኩም ፡ መሠረት ፡ ከጩኺው ፡ ድምፅ ፡ የተነሣ ፡ ተናወጠ ፥ ቤቱንም ፡ ጢስ ፡ ሞላበት ።

5 ፤ እኔም ፦ ከንፈሮቼ ፡ የረከሱብኝ ፡ ሰው ፡ በመኾኔ ፥ ከንፈሮቻቸውም ፡ በረከሱባቸው ፡ ሕዝብ ፡ መካከል ፡ በመቀመጤ ፡ ዐይኖቼ ፡ የሰራዊትን ፡ ጌታ ፡ ንጉሡን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ስለ ፡ አዩ ፡ ጠፍቻለኹና ፡ ወዮልኝ! አልኹ ።

6 ፤ ከሱራፌልም ፡ አንዱ ፡ እየበረረ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ መጣ ፥ በእጁም ፡ ከመሠዊያው ፡ በጕጠት ፡ የወሰደው ፡ ፍም ፡ ነበረ ።

7 ፤ አፌንም ፡ ዳሰሰበትና ፦ እንሆ ፥ ይህ ፡ ከንፈሮችኽን ፡ ነክቷል ፤ በደልኽም ፡ ከአንተ ፡ ተወገደ ፥ ኀጢአትኽም ፡

8 ፤ አውራውም ፡ ፍየል ፡ ራሱን ፡ እጅግ ፡ ታላቅ ፡ አደረገ ፤ በበረታም ፡ ጊዜ ፡ ታላቁ ፡ ቀንዱ ፡ ተሰበረ ፥ ወደ ፡ አራቱም ፡
የሰማይ ፡ ነፋሳት ፡ የሚመለከቱ ፡ አራት ፡ ቀንዶች ፡ ከበታቹ ፡ ወጡ ።

9 ፤ ከነርሱም ፡ ከአንደኛው ፡ አንድ ፡ ታናሽ ፡ ቀንድ ፡ ወጣ ፥ ወደ ፡ ደቡብም ፡ ወደ ፡ ምሥራቅም ፡ ወደ ፡ መልካሚቱም ፡
ምድር ፡ እጅግ ፡ ከፍ ፡ አለ ።

10 ፤ እስከሰማይም ፡ ሰራዊት ፡ ድረስ ፡ ከፍ ፡ አለ ፤ ከሰራዊትና ፡ ከከዋክብትም ፡ ዐያሌዎችን ፡ ወደ ፡ ምድር ፡
ጣለ ፥ ረገጣቸውም ።

11 ፤ እስከሰራዊትም ፡ አለቃ ፡ ድረስ ፡ ራሱን ፡ ታላቅ ፡ አደረገ ፤ ከርሱም ፡ የተነሣ ፡ የዘወትሩ ፡ መሥዋዕት ፡
ተሻረ ፥ የመቅደሱም ፡ ስፍራ ፡ ፈረሰ ።

12 ፤ ሰራዊቱም ፡ ከኀጢአት ፡ የተነሣ ፡ ከዘወትሩ ፡ መሥዋዕት ፡ ጋራ ፡ ተሰጠው ፤ ርሱም ፡ እውነትን ፡ ወደ ፡ ምድሩ ፡
ጣለ ፥ አደረገም ፡ ተከናወነም ።

13 ፤ ከቅዱሳኑም ፡ አንዱ ፡ ሲናገር ፡ ሰማኹ ፤ ለተናገረው ፡ ለቅዱሱም ፡ ኹለተኛው ፡ ቅዱስ ፦ ስለዘወትሩ ፡
መሥዋዕት ፥ መቅደሱና ፡ ሰራዊቱም ፡ ይረገጡ ፡ ዘንድ ፡ ስለሚሰጥና ፡ ስለሚያጠፋ ፡ ኀጢአት ፡ የኾነው ፡ ራእይ ፡ እስከ ፡
መቼ ፡ ይኾናል ፧ አለው ።

14 ፤ ርሱም ፦ እስከ ፡ ኹለት ፡ ሺሕ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ማታና ፡ ጧት ፡ ድረስ ፡ ነው ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ መቅደሱ ፡
ይነጻል ፡ አለኝ ።

15 ፤ እኔም ፡ ዳንኤል ፡ ራእዩን ፡ ባየኹ ፡ ጊዜ ፡ ማስተዋሉን ፡ ፈለግኹ ፤ እንሆም ፥ የሰው ፡ ምስያ ፡ በፊቴ ፡ ቆሞ ፡ ነበር ።

16 ፤ በኡባልም ፡ ወንዝ ፡ መካከል ፦ ገብርኤል[270] ፡ ሆይ ፥ ራእዩን ፡ ለዚህ ፡ ሰው ፡ አስታውቀው ፡ ብሎ ፡ የሚጮኸውን ፡
የሰውን ፡ ድምፅ ፡ ሰማኹ ።

17 ፤ እኔም ፡ ወደ ፡ ቆምኹበት ፡ ቀረበ ፤ በመጣም ፡ ጊዜ ፡ ፈርቼ ፡ በግንባሬ ፡ ተደፋኹ ፤ ርሱም ፦ የሰው ፡ ልጅ ፡
ሆይ ፥ ራእዩ ፡ ለፍጻሜ ፡ ዘመን ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ አስተውል ፡ አለኝ ።

18 ፤ ሲናገረኝም ፡ ደንግጬ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ በግንባሬ ፡ ተደፋኹ ፤ ርሱም ፡ ዳሰሰኝ ፡ ቀጥ ፡ አድርጎም ፡ አቆመኝ ።

19 ፤ እንዲህም ፡ አለኝ ፦ እንሆ ፥ በመቅሠፍቱ ፡ በመጨረሻ ፡ ዘመን ፡ የሚኾነውን ፡ አስታውቅኻለኹ ፤ ይህ ፡
ለተወሰነው ፡ ለፍጻሜ ፡ ዘመን ፡ ነውና ።

20 ፤ ባየኸው ፡ በአውራው ፡ በግ ፡ ላይ ፡ የነበሩ ፡ ኹለቱ ፡ ቀንዶች ፡ እነርሱ ፡ የሜዶንና ፡ የፋርስ ፡ ነገሥታት ፡ ናቸው ።

21 ፤ አውራውም ፡ ፍየል ፡ የግሪክ ፡ ንጉሥ ፡ ነው ፤ በዐይኖቹም ፡ መካከል ፡ ያለው ፡ ታላቁ ፡ ቀንድ ፡ መዠመሪያው ፡
ንጉሥ ፡ ነው ።

22 ፤ ርሱም ፡ በተሰበረ ፡ ጊዜ ፡ በርሱ ፡ ፋንታ ፡ አራቱ ፡ እንደ ፡ ተነሡ ፥ እንዲሁ ፡ ከወገኑ ፡ አራት ፡ መንግሥታት ፡
ይነሣሉ ፥ ነገር ፡ ግን ፥ በኀይል ፡ አይተካከሉትም ።

23 ፤ በመንግሥታቸውም ፡ መጨረሻ ፥ ኀጢአታቸው ፡ በተሞላች ፡ ጊዜ ፥ እንቆቅልሽን ፡ የሚያስተውል ፡ ፊተ ፡ ጨካኝ ፡
ንጉሥ ፡ ይነሣል ።

24 ፤ ኀይሉም ፡ ይበረታል ፥ ነገር ፡ ግን ፥ በራሱ ፡ ኀይል ፡ አይደለም ፤ በድንቅም ፡
ያጠፋል ፥ ያደርግማል ፥ ይከናወንማል ፤ ኀያላንንና ፡ የቅዱሳንን ፡ ሕዝብ ፡ ያጠፋል ።

25 ፤ በመታለሉ ፡ ተንኰልን ፡ በእጁ ፡ ያከናውናል ፤ በልቡም ፡ ይታበያል ፥ ታምነውም ፡ የሚኖሩትን ፡ ብዙዎችን ፡
ያጠፋል ፤ በአለቃዎቹም ፡ አለቃ ፡ ላይ ፡ ይቋቋማል ፤ ያለ ፡ እጅም ፡ ይሰበራል ።

26 ፤ የተነገረውም ፡ የማታውና ፡ የጧቱ ፡ ራእይ ፡ እውነተኛ ፡ ነው ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ከብዙ ፡ ዘመን ፡ በኋላ ፡ ስለሚኾን ፡
ራእዩን ፡ ዝጋ ።

27 ፤ እኔም ፡ ዳንኤል ፡ ተኛኹ ፥ ዐያሌም ፡ ቀን ፡ ታመምኹ ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ተነሥቼ ፡ የንጉሡን ፡ ሥራ ፡ እሠራ ፡

270 ዕብ. ፥ ጋብሪኤል ፡ (ገብረ ፡ እግዚእ • የጌታ ፡ አገልጋይ) ።

ነበር ፤ ስለ ፡ ራእዩም ፡ አደንቅ ፡ ነበር ፥ የሚያስተውለው ፡ ግን ፡ አልነበረም ።

______________________ትንቢተ ፡ ዳንኤል ፥ ምዕራፍ ፡ 9 ። ____________________

ምዕራፍ ፡ 9 ።

1 ፤ በከለዳውያን ፡ መንግሥት ፡ ላይ ፡ በነገሠ ፥ ከሜዶን ፡ ዘር ፡ በነበረ ፡ በአሕሻዊሮስ ፡ ልጅ ፡ በዳርዮስ ፡ በመዠመሪያ ፡ ዓመት ፥

2 ፤ በነገሠ ፡ በመዠመሪያው ፡ ዓመት ፡ እኔ ፡ ዳንኤል ፡ የኢየሩሳሌም ፡ መፍረስ ፡ የሚፈጸምበትን ፡ ሰባውን ፡ ዓመት ፥ እግዚአብሔር ፡ በቃሉ ፡ ለነቢዩ ፡ ለኤርምያስ ፡ የተናገረውን ፡ የዓመቱን ፡ ቍጥር ፡ በመጽሐፍ ፡ አስተዋልኹ ።

3 ፤ ማቅ ፡ ለብሼ ፡ በዐመድም ፡ ላይ ፡ ኾኜ ፡ ስጾም ፡ እጸልይና ፡ እለምን ፡ ዘንድ ፡ ፊቴን ፡ ወደ ፡ ጌታ ፡ ወደ ፡ አምላክ ፡ አቀናኹ ።

4 ፤ ወደ ፡ አምላኬም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸለይኹ ፥ ተናዝዤም ፡ እንዲህ ፡ አልኹ ፦ ጌታ ፡ ሆይ ፥ ከሚወዱኽና ፡ ትእዛዝኽን ፡ ከሚፈጽሙ ፡ ጋራ ፡ ቃል ፡ ኪዳንንና ፡ ምሕረትን ፡ የምትጠብቅ ፡ ታላቅና ፡ የምታስፈራ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፥

5 ፤ ኀጢአትን ፡ ሠርተናል ፥ በድለንማል ፥ ክፋትንም ፡ አድርገናል ፥ ዐምፀንማል ፥ ከትእዛዝኽና ፡ ከፍርድኽም ፡ ፈቀቅ ፡ ብለናል ፤

6 ፤ በስምኽም ፡ ለነገሥታታችንና ፡ ለአለቃዎቻችን ፡ ለአባቶቻችንም ፡ ለአገሩም ፡ ሕዝብ ፡ ዅሉ ፡ የተናገሩትን ፡ ባሪያዎችኽን ፡ ነቢያትን ፡ አልሰማንም ።

7 ፤ ጌታ ፡ ሆይ ፥ ጽድቅ ፡ ለአንተ ፡ ነው ፤ እንደ ፡ ዛሬም ፡ ለእኛ ፡ ለይሁዳ ፡ ሰዎችና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ለሚቀመጡ ፡ ለእስራኤልም ፡ ዅሉ ፡ በቅርብና ፡ በሩቅም ፡ ላሉት ፡ አንተን ፡ በበደሉበት ፡ በበደላቸው ፡ ምክንያት ፡ በበተንኽበት ፡ አገር ፡ ዅሉ ፡ የፊት ፡ ዕፍረት ፡ ነው ።

8 ፤ ጌታ ፡ ሆይ ፥ ባንተ ፡ ላይ ፡ ኀጢአት ፡ ስለ ፡ ሠራን ፡ ለእኛና ፡ ለነገሥታታችን ፡ ለአለቃዎቻችንና ፡ ለአባቶቻችንም ፡ የፊት ፡ ዕፍረት ፡ ነው ።

9 ፤ 10 ፤ በርሱ ፡ ላይ ፡ ምንም ፡ እንኳ ፡ ያመፅን ፡ ብንኾን ፥ በባሪያዎቹም ፡ በነቢያት ፡ እጅ ፡ በፊታችን ፡ ባኖረው ፡ በሕጉ ፡ እንኼድ ፡ ዘንድ ፡ የአምላካችንን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ምንም ፡ እንኳ ፡ ባንሰማ ፥ ለጌታ ፡ ለአምላካችን ፡ ምሕረትና ፡ ይቅርታ ፡ ነው ።

11 ፤ እስራኤልም ፡ ዅሉ ፡ ሕግኽን ፡ ተላልፈዋል ፥ ቃልኽንም ፡ እንዳይሰሙ ፡ ፈቀቅ ፡ ብለዋል ፤ በርሱ ፡ ላይ ፡ ኀጢአት ፡ ሠርተናልና ፥ በእግዚአብሔር ፡ ባሪያ ፡ በሙሴ ፡ ሕግ ፡ የተጻፈው ፡ መሐላና ፡ ርግማን ፡ ፈሰሰብን ።

12 ፤ እጅግ ፡ ክፉ ፡ ነገርንም ፡ በእኛ ፡ ላይ ፡ በማምጣቱ ፡ በላያችንና ፡ በእኛ ፡ ዘንድ ፡ በተሾሙት ፡ ፈራጆቻችን ፡ ላይ ፡ የተናገረውን ፡ ቃል ፡ አጸና ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ ላይ ፡ እንደተደረገው ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ ከቶ ፡ ከሰማይ ፡ ዅሉ ፡ በታች ፡ አልተደረገም ።

13 ፤ በሙሴም ፡ ሕግ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ ይህ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ዅሉ ፡ መጣብን ፤ ከኀጢአታችንም ፡ እንመለስ ፡ እውነትኽንም ፡ እናስብ ፡ ዘንድ ፡ ወደአምላካችን ፡ ወደእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ አልለመንንም ።

14 ፤ ስለዚህም ፡ እግዚአብሔር ፡ ክፉ ፡ ነገሩን ፡ ጠብቆ ፡ በእኛ ፡ ላይ ፡ አመጣ ፤ አምላካችን ፡ እግዚአብሔር ፡ በሚሠራው ፡ ሥራ ፡ ዅሉ ፡ ጻድቅ ፡ ነውና ፥ እኛም ፡ ቃሉን ፡ አልሰማንምና ።

15 ፤ አኹንም ፡ ሕዝብኽን ፡ ከግብጽ ፡ ምድር ፡ በበረታች ፡ እጅ ፡ ያወጣኽ ፥ እንደ ፡ ዛሬም ፡ ቀን ፡ ዝና ፡ ለአንተ ፡ ያገኘኽ ፡ ጌታ ፡ አምላካችን ፡ ሆይ ፥ ኀጢአትን ፡ ሠርተናል ፥ ክፋትንም ፡ አድርገናል ።

16 ፤ ጌታ ፡ ሆይ ፥ ስለ ፡ ኀጢአታችንና ፡ ስላባቶቻችን ፡ በደል ፡ ኢየሩሳሌምና ፡ ሕዝብኽ ፡ በዙሪያችን ፡ ላሉት ፡ ዅሉ ፡ መሰደቢያ ፡ ኾነዋልና ፥ እንደ ፡ ጽድቅኽ ፡ ዅሉ ፡ ቍጣኽና ፡ መዓትኽ ፡ ከከተማኽ ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ከቅዱስ ፡ ተራራኽ ፡ እንዲመለስ ፡ እለምንኻለኹ ።

17 ፤ አኹንም ፥ አምላካችን ፡ ሆይ ፥ የባሪያኽን ፡ ጸሎትና ፡ ልመናውን ፡ ስማ ፤ ጌታ ፡ ሆይ ፥ በፈረሰው ፡ በመቅደስኽ ፡

ላይ ፡ ስለ ፡ አንተ ፡ ስትል ፡ ፊትኽን ፡ አብራ ።

18 ፤ አምላኬ ፡ ሆይ ፥ በፊትኽ ፡ የምንለምን ፡ ስለ ፡ ብዙ ፡ ምሕረትኽ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ስለ ፡ ጽድቃችን ፡ አይደለምና ፡ ዦሮኽን ፡ አዘንብለኽ ፡ ስማ ፤ ዐይንኽን ፡ ገልጠኽ ፡ ጥፋታችንና ፡ ስምኽ ፡ የተጠራባትን ፡ ከተማ ፡ ተመልከት ።

19 ፤ አቤቱ ፥ ስማ ፤ አቤቱ ፥ ይቅር ፡ በል ፤ አቤቱ ፥ አድምጥና ፡ አድርግ ፤ አምላኬ ፡ ሆይ ፥ ስምኽ ፡ በከተማኽና ፡ በሕዝብኽ ፡ ላይ ፡ ተጠርቷልና ፥ ስለ ፡ ራስኽ ፡ አትዘግይ ።

20 ፤ እኔም ፡ ገና ፡ ስናገር ፡ ስጸልይ ፥ በኀጢአቴና ፡ በሕዝቤም ፡ በእስራኤል ፡ ኀጢአት ፡ ስናዘዝ ፥ በአምላኬም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ስለተቀደሰው ፡ ስለአምላኬ ፡ ተራራ ፡ ስለምን ፥

21 ፤ ገናም ፡ በጸሎት ፡ ስናገር ፡ አስቀድሜ ፡ በራእይ ፡ አይቼው ፡ የነበረው ፡ ሰው ፡ ገብርኤል ፥ እንሆ ፥ እየበረረ ፡ መጣ ፤ በማታም ፡ መሥዋዕት ፡ ጊዜ ፡ ዳሰሰኝ ።

22 ፤ አስተማረኝም ፥ ተናገረኝም ፡ እንዲህም ፡ አለ ፦ ዳንኤል ፡ ሆይ ፥ ጥበብንና ፡ ማስተዋልን ፡ እሰጥኽ ፡ ዘንድ ፡ አኹን ፡ መጥቻለኹ ።

23 ፤ አንተ ፡ እጅግ ፡ የተወደድኽ ፡ ነኽና ፥ በልመናኽ ፡ መዠመሪያ ፡ ላይ ፡ ትእዛዝ ፡ ወጥቷል ፥ እኔም ፡ እነግርኽ ፡ ዘንድ ፡ መጥቻለኹ ፤ አኹንም ፡ ነገሩን ፡ መርምር ፥ ራእዩንም ፡ አስተውል ።

24 ፤ ዐመፃን ፡ ይጨርስ ፥ ኀጢአትንም ፡ ይፈጽም ፥ በደልንም ፡ ያስተሰርይ ፥ የዘለዓለምን ፡ ጽድቅ ፡ ያገባ ፥ ራእይንና ፡ ትንቢትን ፡ ያትም ፥ ቅዱሰ ፡ ቅዱሳኑንም ፡ ይቀባ ፡ ዘንድ ፡ በሕዝብኽና ፡ በቅድስት ፡ ከተማኽ ፡ ላይ ፡ ሰባ ፡ ሱባዔ ፡ ተቀጥሯል ።

25 ፤ ስለዚህ ፥ ዕወቅ ፡ አስተውልም ፤ ኢየሩሳሌምን ፡ መጠገንና ፡ መሥራት ፡ ትእዛዙ ፡ ከሚወጣበት ፡ ዠምሮ ፡ እስከ ፡ አለቃው ፡ እስከ ፡ መሲሕ ፡ ድረስ ፡ ሰባት ፡ ሱባዔና ፡ ስድሳ ፡ ኹለት ፡ ሱባዔ ፡ ይኾናል ፤ ርሷም ፡ በጭንቀት ፡ ዘመን ፡ ከጐዳናና ፡ ከቅጥር ፡ ጋራ ፡ ትሠራለች ።

26 ፤ ከስድሳ ፡ ኹለት ፡ ጊዜ ፡ ሰባትም ፡ በዃላ ፡ መሲሕ ፡ ይገደላል ፥ በርሱም ፡ ዘንድ ፡ ምንም ፡ የለም ፤ የሚመጣውም ፡ አለቃ ፡ ሕዝብ ፡ ከተማዪቱንና ፡ መቅደሱን ፡ ያጠፋሉ ፤ ፍጻሜውም ፡ በጐርፍ ፡ ይኾናል ፥ እስከ ፡ መጨረሻም ፡ ድረስ ፡ ጦርነት ፡ ይኾናል ፤ ጥፋትም ፡ ተቀጥሯል ።

27 ፤ ርሱም ፡ ከብዙ ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ ጽኑ ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ላንድ ፡ ሱባዔ ፡ ያደርጋል ፤ በሱባዔውም ፡ እኩሌታ ፡ መሥዋዕቱንና ፡ ቍርባኑን ፡ ያስቀራል ፤ በርኵሰትም ፡ ጫፍ ፡ ላይ ፡ አጥፊው ፡ ይመጣል ፤ እስከተቈረጠውም ፡ ፍጻሜ ፡ ድረስ ፡ መቅሠፍት ፡ በአጥፊው ፡ ላይ ፡ ይፈሳል ።

ትንቢተ ፡ ዳንኤል ፥ ምዕራፍ ፡ 10 ።

ምዕራፍ ፡ 10 ።

1 ፤ በፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ በቂሮስ ፡ በሦስተኛው ፡ ዓመት ፡ ብልጣሶር ፡ ለተባለው ፡ ለዳንኤል ፡ ነገር ፡ ተገለጠለት ፤ ነገሩም ፡ እውነት ፡ ነበረ ፥ ርሱም ፡ ታላቅ ፡ ጦርነት ፡ ነው ፤ ነገሩንም ፡ አስተዋለ ፥ በራእዩም ፡ ውስጥ ፡ ማስተዋል ፡ ተሰጠው ።

2 ፤ በዚያም ፡ ወራት ፡ እኔ ፡ ዳንኤል ፡ ሦስት ፡ ሳምንት ፡ ሙሉ ፡ ሳዝን ፡ ነበር ።

3 ፤ ማለፊያ ፡ እንጀራም ፡ አልበላኹም ፥ ሥጋና ፡ ጠጅም ፡ በአፌ ፡ አልገባም ፥ ሦስቱም ፡ ሳምንት ፡ እስኪፈጸም ፡ ድረስ ፡ ዘይት ፡ አልተቀባኹም ።

4 ፤ ከመዠመሪያውም ፡ ወር ፡ በኻያ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ ጤግሮስ ፡ በተባለው ፡ በታላቁ ፡ ወንዝ ፡ አጠገብ ፡ ሳለኹ ፥ ዐይኔን ፡ አነሣኹ ፥

5 ፤ እንሆም ፥ በፍታ ፡ የለበሰውን ፡ ጥሩም ፡ የአፌዝን ፡ ወርቅ ፡ በወገቡ ፡ ላይ ፡ የታጠቀውን ፡ ሰው ፡ አየኹ ።

6 ፤ አካሉም ፡ እንደ ፡ ቢረሌ ፡ ይመስል ፡ ነበር ፥ ፊቱም ፡ እንደ ፡ መብረቅ ፡ ምስያ ፡ ነበረ ፥ ዐይኖቹም ፡ እንደሚንበለበል ፡ ፋና ፥ ክንዶቹና ፡ እግሮቹም ፡ እንደ ፡ ጋለ ፡ ናስ ፥ የቃሉም ፡ ድምፅ ፡ እንደ ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ድምፅ ፡ ነበረ ።

7 ፤ እኔም ፡ ዳንኤል ፡ ብቻዬን ፡ ራእዩን ፡ አየኹ ፥ ከእኔ ፡ ጋራ ፡ የነበሩ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ራእዩን ፡ አላዩም ፤ ነገር ፡

ግን ፥ ጽኑ ፡ መንቀጥቀጥ ፡ ወደቀባቸው ፥ ሊሸሸጉም ፡ ሸሹ ።

8 ፤ እኔም ፡ ብቻዬን ፡ ቀረኹ ፡ ይህንም ፡ ታላቅ ፡ ራእይ ፡ አየኹ ፤ ኀይልም ፡ አልቀረልኝም ፥ ደም ፡ ግባቴም ፡ ወደ ፡ ማሸብሸብ ፡ ተለወጠብኝ ፥ ኀይልም ፡ ዐጣኹ ።

9 ፤ የቃሉንም ፡ ድምፅ ፡ ሰማኹ ፤ የቃሉንም ፡ ድምፅ ፡ በሰማኹ ፡ ጊዜ ፡ ደንግጬ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ በግንባሬ ፡ ተደፋኹ ።

10 ፤ እንሆም ፥ አንዲት ፡ እጅ ፡ ዳሰሰችኝ ፥ በጕልበቴና ፡ በእጄም ፡ አቆመችኝ ።

11 ፤ ርሱም ፦ እጅግ ፡ የተወደድኽ ፡ ሰው ፡ ዳንኤል ፡ ሆይ ፥ እኔ ፡ ዛሬ ፡ ወዳንተ ፡ ተልኬያለኹና ፡ የምነግርኽን ፡ ቃል ፡ አስተውል ፥ ቀጥ ፡ ብለኽም ፡ ቁም ፡ አለኝ ። ይህንም ፡ ቃል ፡ ባለኝ ፡ ጊዜ ፡ እየተንቀጠቀጥኹ ፡ ቆምኹ ።

12 ፤ ርሱም ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፦ ዳንኤል ፡ ሆይ ፥ አትፍራ ፤ ልብኽ ፡ ያስተውል ፡ ዘንድ ፥ ሰውነትኽም ፡ በአምላክኽ ፡ ፊት ፡ ይዋረድ ፡ ዘንድ ፡ ካደረግኽበት ፡ ከመዠመሪያው ፡ ቀን ፡ ዠምሮ ፡ ቃልኽ ፡ ተሰምቷል ፤ እኔም ፡ ስለ ፡ ቃልኽ ፡ መጥቻለኹ ።

13 ፤ የፋርስ ፡ መንግሥት ፡ አለቃ ፡ ግን ፡ ኻያ ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ተቋቋመኝ ፤ እንሆም ፥ ከዋነኞዎቹ ፡ አለቃዎች ፡ አንዱ ፡ ሚካኤል ፡ ሊረዳኝ ፡ መጣ ፤ እኔም ፡ ከፋርስ ፡ ነገሥታት ፡ ጋራ ፡ በዚያ ፡ ተውኹት ።

14 ፤ ራእዩም ፡ ገና ፡ ለብዙ ፡ ዘመን ፡ ነውና ፥ በኋለኛው ፡ ዘመን ፡ ለሕዝብኽ ፡ የሚኾነውን ፡ አስታውቅኽ ፡ ዘንድ ፡ አኹን ፡ መጥቻለኹ ።

15 ፤ ይህንም ፡ ቃል ፡ በተናገረኝ ፡ ጊዜ ፡ ፊቴን ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ አቀረቀርኹ ፥ ዲዳም ፡ ኾንኹ ።

16 ፤ እንሆም ፥ የሰው ፡ ልጅ ፡ የሚመስል ፡ ከንፈሬን ፡ ዳሰሰኝ ፤ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ አፌን ፡ ከፍቼ ፡ ተናገርኹ ፡ በፊቴም ፡ ቆሞ ፡ የነበረውን ፦ ጌታዬ ፡ ሆይ ፥ ከራእዩ ፡ የተነሣ ፡ ሕመሜ ፡ መጣብኝ ፥ ኀይልም ፡ ዐጣኹ ።

17 ፤ ይህ ፡ የጌታዬ ፡ ባሪያ ፡ ከዚህ ፡ ከጌታዬ ፡ ጋራ ፡ ይናገር ፡ ዘንድ ፡ እንዴት ፡ ይችላል ፤ አኹንም ፡ ኀይል ፡ ዐጣኹ ፥ እስትንፋስም ፡ አልቀረልኝም ፡ አልኹት ።

18 ፤ ደግሞ ፡ ሰው ፡ የሚመስል ፡ ዳሰሰኝ ፥ አበረታኝም ።

19 ፤ ርሱም ፦ እጅግ ፡ የተወደድኽ ፡ ሰው ፡ ሆይ ፥ አትፍራ ፤ ሰላም ፡ ለአንተ ፡ ይኹን ፤ በርታ ፥ ጽና ፡ አለኝ ። በተናገረኝም ፡ ጊዜ ፡ በረታኹና ፦ አበርትተኸኛልና ፥ ጌታዬ ፡ ይናገር ፡ አልኹ ።

20 ፤ ርሱም ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፦ ወዳንተ ፡ የመጣኹት ፡ ስለ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ኾነ ፥ ታውቃለኽን ፤ አኹንም ፡ ከፋርስ ፡ አለቃ ፡ ጋራ ፡ እዋጋ ፡ ዘንድ ፡ እመለሳለኹ ፤ እኔም ፡ ስወጣ ፥ እንሆ ፤ የግሪክ ፡ አለቃ ፡ ይመጣል ።

21 ፤ ነገር ፡ ግን ፥ በእውነት ፡ ጽሑፍ ፡ የተጻፈውን ፡ እነግርኻለኹ ፤ በዚህም ፡ ነገር ፡ ከአለቃችኹ ፡ ከሚካኤል ፡ በቀር ፡ ማንም ፡ የሚያጸናኝ ፡ የለም ።

## ትንቢተ ፡ ዳንኤል ፥ ምዕራፍ ፡ 11 ።

ምዕራፍ ፡ 11 ።

1 ፤ እኔም ፡ በሜዶናዊ ፡ በዳርዮስ ፡ መዠመሪያ ፡ ዓመት ፡ አጸናውና ፡ አበረታው ፡ ዘንድ ፡ ቆሜ ፡ ነበር ።

2 ፤ አኹንም ፡ እውነትን ፡ አሳይኻለኹ ። እንሆ ፥ ሦስት ፡ ነገሥታት ፡ ደግሞ ፡ በፋርስ ፡ ይነሣሉ ፤ አራተኛውም ፡ ከኹሉ ፡ ይልቅ ፡ እጅግ ፡ ባለጠጋ ፡ ይኾናል ፤ በባለጠግነቱም ፡ በበረታ ፡ ጊዜ ፡ በግሪክ ፡ መንግሥት ፡ ላይ ፡ ኹሉን ፡ ያስነሣል ።

3 ፤ ኀያልም ፡ ንጉሥ ፡ ይነሣል ፥ በትልቅ ፡ አገዛዝም ፡ ይገዛል ፥ እንደ ፡ ፈቃዱም ፡ ያደርጋል ።

4 ፤ ርሱም ፡ በተነሣ ፡ ጊዜ ፡ መንግሥቱ ፡ ይሰበራል ፤ እስከ ፡ አራቱ ፡ የሰማይ ፡ ነፋሳት ፡ ይከፋፈላል ። ለዘሩ ፡ ግን ፡ አይከፋፈልም ፥ እንደ ፡ ገዛበትም ፡ አገዛዝ ፡ አይኾንም ፤ መንግሥቱ ፡ ይነቀላልና ፤ ከነዚህም ፡ ለሌላዎች ፡ ይኾናልና ።

5 ፤ የደቡብም ፡ ንጉሥ ፡ ከአለቃዎቹም ፡ አንዱ ፡ ይበረታሉ ፤ ርሱም ፡ ይበረታበታል ፡ ይሠለጥንማል ፤ ግዛቱም ፡ ታላቅ ፡ ግዛት ፡ ይኾናል ።

6 ፤ ከዘመናትም ፡ በኋላ ፡ ይጋጠማሉ ፤ የደቡብም ፡ ንጉሥ ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ለማድረግ ፡ ወደሰሜን ፡ ንጉሥ ፡

ትመጣለች ፤ የክንዷ ፡ ኀይል ፡ ግን ፡ አይጸናም ፥ ርሱና ፡ ክንዱም ፡ አይጸናም ፤ ርሷና ፡ ርሷን ፡ ያመጡ ፡ የወለዳትም ፡
በዚያም ፡ ዘመን ፡ ያጸናት ፡ ዐልፈው ፡ ይሰጣሉ ።

7 ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ከሥሯ ፡ ቍጥቋጥ ፡ አንዱ ፡ በስፍራው ፡ ይነሣል ፤ ወደ ፡ ሰራዊቱም ፡ ይመጣል ፥ ወደሰሜንም ፡ ንጉሥ ፡
ዐምባ ፡ ይገባል ፥ በላያቸውም ፡ ያደርጋል ፥ ያሸንፍማል ።

8 ፤ አማልክታቸውንና ፡ ቀልጠው ፡ የተሠሩትን ፡ ምስሎቻቸውን ፡ ከብርና ፡ ከወርቅም ፡ የተሠሩትን ፡ የከበሩትን ፡
ዕቃዎች ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ ይማርካል ፤ እስከ ፡ ጥቂትም ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡ ከሰሜን ፡ ንጉሥ ፡ ጋራ ፡ ሳይዋጋ ፡ ይቀመጣል ።

9 ፤ ይህም ፡ ወደደቡብ ፡ ንጉሥ ፡ መንግሥት ፡ ይገባል ፥ ነገር ፡ ግን ፥ ወደገዛ ፡ ምድሩ ፡ ይመለሳል ።

10 ፤ ልጆቹም ፡ ይዋጋሉ ፤ ብዙ ፡ ሰራዊትንና ፡ ሕዝብን ፡ ይሰበስባል ፤ ርሱም ፡
ይመጣል ፥ ይጐርፍማል ፥ ያልፍማል ፤ ተመልሶም ፡ እስከ ፡ ዐምባው ፡ ድረስ ፡ ይዋጋል ።

11 ፤ የደቡብም ፡ ንጉሥ ፡ ይቈጣል ፡ ወጥቶም ፡ ከሰሜን ፡ ንጉሥ ፡ ጋራ ፡ ይዋጋል ፤ ብዙ ፡ ሕዝብንም ፡ ለሰልፍ ፡
ያቆማል ፥ ሕዝቡም ፡ ዐልፎ ፡ በእጁ ፡ ይሰጣል ።

12 ፤ ሕዝቡም ፡ በተወሰደ ፡ ጊዜ ፡ ልቡ ፡ ይታበያል ፤ አእላፋትንም ፡ ይጥላል ፥ ነገር ፡ ግን ፥ አያሸንፍም ።

13 ፤ የሰሜንም ፡ ንጉሥ ፡ ይመለሳል ፥ ከቀደመውም ፡ የበለጠ ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ለሰልፍ ፡ ያቆማል ፤ በዘመናትና ፡
በዓመታትም ፡ ፍጻሜ ፡ ከታላቅ ፡ ሰራዊትና ፡ ከብዙ ፡ ሀብት ፡ ጋራ ፡ ይመጣል ።

14 ፤ በዚያም ፡ ዘመን ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ በደቡብ ፡ ንጉሥ ፡ ላይ ፡ ይነሣሉ ፤ ከሕዝብኽም ፡ መካከል ፡ የዐመፅ ፡ ልጆች ፡
ራእዩን ፡ ያጸኑ ፡ ዘንድ ፡ ይነሣሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ይወድቃሉ ።

15 ፤ የሰሜንም ፡ ንጉሥ ፡ ይመጣል ፥ ዐፈርንም ፡ ይደለድላል ፥ የተመሸገችንም ፡ ከተማ ፡ ይወስዳል ፤ የደቡብም ፡
ሰራዊት ፡ የተመረጡትም ፡ ሕዝቡ ፡ አይቆሙም ፤ ለመቋቋምም ፡ ኀይል ፡ የላቸውም ።

16 ፤ በርሱም ፡ ላይ ፡ የሚመጣው ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ፈቃዱ ፡ ያደርጋል ፥ በፊቱም ፡ የሚቆም ፡ የለም ፤ በመልካሚቱም ፡
ምድር ፡ ይቆማል ፥ በእጁም ፡ ውስጥ ፡ ጥፋት ፡ ይኾናል ።

17 ፤ ከመንግሥቱም ፡ ኹሉ ፡ ኀይል ፡ ጋራ ፡ ይመጣ ፡ ዘንድ ፡ ፊቱን ፡ ያቀናል ፥ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ አንድነትን ፡
ያደርጋል ፤ ያረክሳትም ፡ ዘንድ ፡ ሴትን ፡ ልጅ ፡ ይሰጠዋል ፤ ርሷም ፡ አትጸናም ፡ ለርሱም ፡ አትኾንም ።

18 ፤ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ፊቱን ፡ ወደ ፡ ደሴቶች ፡ ይመልሳል ፥ ብዙዎችንም ፡ ይወስዳል ፤ አንድ ፡ አለቃ ፡ ግን ፡ ስድቡን ፡
ይሽራል ፥ ስድቡንም ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ይመልሳል ።

19 ፤ ፊቱንም ፡ ወደገዛ ፡ ምድሩ ፡ ዐምባዎች ፡ ይመልሳል ፤ ተሰናክሎም ፡ ይወድቃል ፥ አይገኝምም ።

20 ፤ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ በመንግሥቱ ፡ ክብር ፡ መካከል ፡ አስገባሪውን ፡ የሚያሳልፍ ፡ በስፍራው ፡ ይነሣል ፤ ነገር ፡
ግን ፥ በቍጣው ፡ ሳይኾን ፡ በሰልፍም ፡ ሳይኾን ፡ በጥቂት ፡ ቀን ፡ ይሰበራል ።

21 ፤ በርሱም ፡ ስፍራ ፡ የተጠቃ ፡ ሰው ፡ ይነሣል ፡ የመንግሥቱንም ፡ ክብር ፡ አይሰጡትም ፤ በቀስታ ፡ መጥቶ ፡
መንግሥቱን ፡ በማታለል ፡ ይገዛል ።

22 ፤ የሚጐርፍም ፡ ሰራዊት ፡ ከፊቱ ፡ ይወሰዳል ፥ ርሱና ፡ የቃል ፡ ኪዳኑ ፡ አለቃ ፡ ይሰበራሉ ።

23 ፤ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ ከተወዳጀ ፡ በኋላ ፥ በተንኰል ፡ ያደርጋል ፤ ከጥቂትም ፡ ሕዝብ ፡ ጋራ ፡ ወጥቶ ፡ ይበረታል ።

24 ፤ በቀስታ ፡ ከአገር ፡ ኹሉ ፡ ወደለመለመችው ፡ ክፍል ፡ ይገባል ፤ አባቶቹና ፡ የአባቶቹ ፡ አባቶች ፡ ያላደረጉትንም ፡
ያደርጋል ፤ ብዝበዛውንና ፡ ምርኮውንም ፣ ሀብቱንም ፡ በመካከላቸው ፡ ይበትናል ፤ በምሽጎችም ፡ ላይ ፡ እስከ ፡ ጊዜው ፡
ድረስ ፡ ዐሳቡን ፡ ይፈጥራል ።

25 ፤ በታላቅም ፡ ሰራዊት ፡ ኃና ፡ ኀይሉንና ፡ ልቡን ፡ በደቡብ ፡ ንጉሥ ፡ ላይ ፡ ያስነሣል ፤ የደቡብም ፡ ንጉሥ ፡ በታላቅና ፡
በብዙ ፡ ሰራዊት ፡ ኃና ፡ በሰልፍ ፡ ይዋጋል ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ዐሳብ ፡ በርሱ ፡ ላይ ፡ ይፈጥራሉና ፥ አይጸናም ።

26 ፤ መብሉንም ፡ የሚበሉ ፡ ሰዎች ፡ ይሰብሩታል ፤ ሰራዊቱም ፡ ይጐርፋል ፤ ብዙዎችም ፡ ተገድለው ፡ ይወድቃሉ ።

27 ፤ እነዚህም ፡ ኹለት ፡ ነገሥታት ፡ ክፋትን ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ በልባቸው ፡ ያስባሉ ፥ ባንድ ፡ ገበታም ፡ ተቀምጠው ፡
ሐሰት ፡ ይናገራሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ፍጻሜው ፡ እስከተወሰነው ፡ ጊዜ ፡ ነውና ፥ አይከናወንላቸውም ።

28 ፤ ከብዙም ፡ ሀብት ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ ምድሩ ፡ ይመለሳል ፥ ልቡም ፡ በተቀደሰ ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ላይ ፡
ይኾናል ፤ ፈቃዱንም ፡ ያደርጋል ፥ ወደገዛ ፡ ምድሩም ፡ ይመለሳል ።

29 ፤ በተወሰነውም ፡ ጊዜ ፡ ይመለሳል ፥ ወደ ፡ ደቡብም ፡ ይመጣል ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ኋለኛው ፡ እንደ ፡ ፊተኛው ፡
አይኾንም ።

30 ፤ የኪቲም ፡ መርከቦች ፡ ይመጡበታልና ፥ ስለዚህ ፡ ዐዝኖ ፡ ይመለሳል ፥ በቅዱሱም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ላይ ፡
ይቈጣል ፥ ፈቃዱንም ፡ ያደርጋል ፤ ተመልሶም ፡ ቅዱሱን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ የተዉትን ፡ ሰዎች ፡ ይመለከታል ።

31 ፤ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ ሰራዊቶች ፡ ይቆማሉ ፥ መቅደሱንም ፣ ግንቡንም ፡ ያረክሳሉ ፥ የዘወትሩንም ፡ መሥዋዕት ፡
ያስቀራሉ ፥ የጥፋትንም ፡ ርኵሰት ፡ ያቆማሉ ።

32 ፤ ቃል ፡ ኪዳኑን ፡ የሚበድሉትንም ፡ በማታለል ፡ ያስታል ፤ ነገር ፡ ግን ፥ አምላካቸውን ፡ የሚያውቁ ፡ ሕዝብ ፡
ይበረታሉ ፥ ያደርጋሉም ።

33 ፤ በሕዝቡም ፡ መካከል ፡ ያሉ ፡ ጥበበኛዎች ፡ ብዙ ፡ ሰዎችን ፡ ያስተምራሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፥ በሰይፍና ፡ በእሳት ፡
ነበልባል ፡ በምርኮና ፡ በመበዝበዝ ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ ይወድቃሉ ።

34 ፤ በወደቁም ፡ ጊዜ ፡ በጥቂት ፡ ርዳታ ፡ ይረዳሉ ፤ ብዙ ፡ ሰዎችም ፡ በግብዝነት ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ተባብረው ፡
ይሰበሰባሉ ።

35 ፤ እስከተወሰነውም ፡ ዘመን ፡ ይኾናልና ፥ ከጥበበኛዎቹ ፡ ዐያሌዎቹ ፡ እስከ ፡ ፍጻሜ ፡ ዘመን ፡ ይነጥሩና ፡
ይጠሩ ፣ ይነጡም ፡ ዘንድ ፡ ይወድቃሉ ።

36 ፤ ንጉሡም ፡ እንደ ፡ ፈቃዱ ፡ ያደርጋል ፤ ራሱንም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደርጋል ፥ በአማልክት ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፡ ራሱን ፡
ታላቅ ፡ ያደርጋል ፥ በአማልክትም ፡ አምላክ ፡ ላይ ፡ በትዕቢት ፡ ይናገራል ፤ ቍጣም ፡ እስኪፈጸም ፡ ድረስ ፡
ይከናወንለታል ፥ የተወሰነው ፡ ይደረጋልና ።

37 ፤ የአባቶቹንም ፡ አማልክት ፡ የሴቶችንም ፡ ምኞት ፡ አይመለከትም ፤ ራሱንም ፡ በኹሉ ፡ ላይ ፡ ታላቅ ፡
ያደርጋልና ፥ አማልክትን ፡ ኹሉ ፡ አይመለከትም ።

38 ፤ በእነዚህ ፡ ፋንታ ፡ ግን ፡ የዐምባዎቹን ፡ አምላክ ፡ ያከብራል ፤ አባቶቹም ፡ ያላወቁትን ፡ አምላክ ፡ በወርቅና ፡ በብር ፡
በዕንቍና ፡ በከበረ ፡ ነገር ፡ ያከብረዋል ።

39 ፤ በእንግዳም ፡ አምላክ ፡ ርዳታ ፡ በጽኑ ፡ ዐምባ ፡ ላይ ፡ ያደርጋል ፤ ለሚያውቁት ፡ ክብር ፡ ያበዛላቸዋል ፥ በብዙም ፡
ላይ ፡ ያስገዛቸዋል ፥ ምድርንም ፡ በዋጋ ፡ ይከፍላል ።

40 ፤ በፍጻሜ ፡ ዘመንም ፡ የደቡብ ፡ ንጉሥ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ይዋጋል ፤ የሰሜንም ፡ ንጉሥ ፡ ከሠረገላዎችና ፡
ከፈረሰኛዎች ፡ ከብዙም ፡ መርከቦች ፡ ጋራ ፡ እንደ ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ ይመጣበታል ፤ ወደ ፡ አገሮችም ፡
ይገባል ፥ ይጕርፍማል ፥ ያልፍማል ።

41 ፤ ወደ ፡ መልካሚቱም ፡ ምድር ፡ ይገባል ፥ ብዙ ፡ አገሮችም ፡ ይወድቃሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ኤዶምያስና ፡ ሞዐብ ፡
ከዐሞንም ፡ ልጆች ፡ የበለጡት ፡ ከእጁ ፡ ይድናሉ ።

42 ፤ እጁን ፡ በአገሮች ፡ ላይ ፡ ይዘረጋል ፥ የግብጽም ፡ ምድር ፡ አታመልጥም ።

43 ፤ በወርቅና ፡ በብርም ፡ መዝገብ ፡ ላይ ፥ በከበረችም ፡ በግብጽ ፡ ዕቃ ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፡ ይሠለጥናል ፤ የልብያና ፡
የኢትዮጵያ ፡ ሰዎችም ፡ ይከተሉታል ።

44 ፤ ከምሥራቅና ፡ ከሰሜን ፡ ግን ፡ ወሬ ፡ ያውከዋል ፤ ብዙ ፡ ሰዎችንም ፡ ይገድል ፡ ዘንድና ፡ ፈጽሞ ፡ ያጠፋ ፡ ዘንድ ፡
በታላቅ ፡ ቍጣ ፡ ይወጣል ።

45 ፤ ንጉሣዊ ፡ ድንኳኑንም ፡ በባሕርና ፡ በከበረው ፡ በቅዱስ ፡ ተራራ ፡ መካከል ፡ ይተክላል ፤ ወደ ፡ ፍጻሜው ፡ ግን ፡

ይመጣል ፥ ማንም ፡ አይረዳውም ።

## ትንቢተ ፡ ዳንኤል ፥ ምዕራፍ ፡ 12 ።

ምዕራፍ ፡ 12 ።

1 ፤ በዚያም ፡ ዘመን ፡ ስለሕዝብኽ ፡ ልጆች ፡ የሚቆመው ፡ ታላቁ ፡ አለቃ ፡ ሚካኤል ፡ ይነሣል ፤ ሕዝብም ፡ ከኾነ ፡
ዠምሮ ፡ እስከዚያ ፡ ዘመን ፡ ድረስ ፡ እንደ ፡ ርሱ ፡ ያለ ፡ ያልኾነ ፡ የመከራ ፡ ዘመን ፡ ይኾናል ፤ በዚያም ፡ ዘመን ፡
በመጽሐፉ ፡ ተጽፎ ፡ የተገኘው ፡ ሕዝብኽ ፡ ዅሉ ፡ እያንዳንዱ ፡ ይድናል ።

2 ፤ በምድርም ፡ ትቢያ ፡ ውስጥ ፡ ካንቀላፉቱ ፡ ብዙዎች ፡ ይነቃሉ ፤ እኩሌቶቹ ፡ ወደዘለዓለም ፡ ሕይወት ፥ እኩሌቶቹም ፡
ወደ ፡ ዕፍረትና ፡ ወደዘለዓለም ፡ ጕስቍልና ።

3 ፤ ጥበበኛዎቹም ፡ እንደሰማይ ፡ ጸዳል ፥ ብዙ ፡ ሰዎችንም ፡ ወደ ፡ ጽድቅ ፡ የሚመልሱ ፡ እንደ ፡ ከዋክብት ፡ ለዘለዓለም ፡
ይደምቃሉ ።

4 ፤ ዳንኤል ፡ ሆይ ፥ አንተ ፡ ግን ፡ እስከ ፡ ፍጻሜ ፡ ዘመን ፡ ድረስ ፡ ቃሉን ፡ ዝጋ ፥ መጽሐፉንም ፡ ዐትም ፤ ብዙ ፡ ሰዎች ፡
ይመረምራሉ ፥ ዕውቀትም ፡ ይበዛል ።

5 ፤ እኔም ፡ ዳንኤል ፡ አየኹ ፤ እንሆም ፥ ኹለት ፡ ሌላዎች ፡ ቆመው ፡ ነበር ፥ አንዱ ፡ በዚህ ፡ በወንዙ ፡ ዳር ፥ ሌላውም ፡
በዚያ ፡ በወንዙ ፡ ዳር ።

6 ፤ አንዱም ፡ ከወንዙ ፡ ውሃ ፡ በላይ ፡ የነበረውን ፡ በፍታም ፡ የለበሰውን ፦ የዚህ ፡ ድንቅ ፡ ፍጻሜ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡
ነው ፧ አለው ።

7 ፤ ከወንዙም ፡ ውሃ ፡ በላይ ፡ የነበረው ፡ በፍታም ፡ የለበሰው ፡ ሰው ፡ ቀኝና ፡ ግራ ፡ እጁን ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡
አንሥቶ ፦ ለዘመንና ፡ ለዘመናት ፡ ለዘመንም ፡ እኩሌታ ፡ ነው ፤ የተቀደሰውም ፡ ሕዝብ ፡ ኀይል ፡ መበተን ፡ በተጨረሰ ፡
ጊዜ ፡ ይህ ፡ ዅሉ ፡ ይፈጸማል ፡ ብሎ ፡ ለዘለዓለም ፡ ሕያው ፡ ኾኖ ፡ በሚኖረው ፡ ሲምል ፡ ሰማኹ ።

8 ፤ ሰማኹም ፥ ነገር ፡ ግን ፥ አላስተዋልኹም ፤ የዚያን ፡ ጊዜም ፦ ጌታዬ ፡ ሆይ ፥ የዚህ ፡ ዅሉ ፡ ፍጻሜ ፡ ምንድር ፡
ነው ፧ አልኹ ።

9 ፤ ርሱም ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፦ ዳንኤል ፡ ሆይ ፥ ቃሉ ፡ እስከ ፡ ፍጻሜ ፡ ዘመን ፡ ድረስ ፡ የተዘጋና ፡ የታተመ ፡
ነውና ፥ ኺድ ፤

10 ፤ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ሰውነታቸውን ፡ ያጠራሉ ፥ ያነጡማል ፥ ይነጥሩማል ፤ ክፉዎች ፡ ግን ፡ ክፋትን ፡
ያደርጋሉ ፤ ክፉዎችም ፡ ዅሉ ፡ አያስተውሉም ፥ ጥበበኛዎች ፡ ግን ፡ ያስተውላሉ ።

11 ፤ የዘወትሩም ፡ መሥዋዕት ፡ ከቀረ ፡ ዠምሮ ፥ የጥፋትም ፡ ርኵሰት ፡ ከቆመ ፡ ዠምሮ ፡ ሺሕ ፡ ኹለት ፡ መቶ ፡ ዘጠና ፡
ቀን ፡ ይኾናል ።

12 ፤ የሚታገሥ ፥ እስከ ፡ ሺሕ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ዐምስት ፡ ቀንም ፡ የሚደርስ ፡ ምስጉን ፡ ነው ።

13 ፤ አንተ ፡ ግን ፡ እስከ ፡ ፍጻሜው ፡ ድረስ ፡ ኺድ ፤ አንተም ፡ ታርፋለኽ ፥ በቀኑም ፡ መጨረሻ ፡ በዕጣ ፡ ክፍልኽ ፡
ትቆማለኽ ፨

# ትንቢተ ፡ ሆሴዕ ።

(ክለሳ.1.20020507)

ትንቢተ ፡ ሆሴዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 1 ።

ምዕራፍ ፡ 1 ።

1 ፤ በይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ በዖዝያንና ፡ በኢዮአታም ፡ በአካዝና ፡ በሕዝቅያስም ፡ ዘመን ፡ በእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ በዮአስ ፡
ልጅ ፡ በኢዮርብዓም ፡ ዘመን ፡ ወደብኤሪ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ሆሴዕ ፡ የመጣ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ፦

2 ፤ እግዚአብሔር ፡ መዠመሪያ ፡ በሆሴዕ ፡ በተናገረ ፡ ጊዜ ፥ እግዚአብሔር ፡ ሆሴዕን ፦ ምድሪቱ ፡ ከእግዚአብሔር ፡
ርቃ ፡ ታላቅ ፡ ግልሙትና ፡ ታደርጋለችና ፡ ኺድ ፤ ጋለሞታን ፡ ሴትና ፡ የግልሙትናን ፡ ልጆች ፡ ለአንተ ፡ ውሰድ ፡
አለው ።

3 ፤ ርሱም ፡ ኼዶ ፡ የዴቤላይምን ፡ ልጅ ፡ ጎሜርን ፡ አገባ ፤ ርሷም ፡ ፀነሰች ፡ ወንድ ፡ ልጅንም ፡ ወለደችለት ።

4 ፤ እግዚአብሔርም ፦ ከጥቂት ፡ ዘመን ፡ በዃላ ፡ የኢይዝራኤልን ፡ ደም ፡ በኢዩ ፡ ቤት ፡ ላይ ፡
እበቀላለኹና ፥ ከእስራኤልም ፡ ቤት ፡ መንግሥትን ፡ እሽራለኹና ፡ ስሙን ፡ ኢይዝራኤል ፡ ብለኽ ፡ ጥራው ፤

5 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ በኢይዝራኤል ፡ ሸለቆ ፡ ውስጥ ፡ የእስራኤልን ፡ ቀስት ፡ እሰብራለኹ ፡ አለው ።

6 ፤ ደግሞ ፡ ፀነሰች ፡ ሴት ፡ ልጅንም ፡ ወለደች ። እግዚአብሔርም ፦ ይቅር ፡ እላቸው ፡ ዘንድ ፡ የእስራኤልን ፡ ቤት ፡
ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አልምርምና ፡ ስሟን ፡ ሎሩሃማ ፡ ብለኽ ፡ ጥራት ፤

7 ፤ ነገር ፡ ግን ፥ የይሁዳን ፡ ቤት ፡ እምራለኹ ፤ በአምላካቸውም ፡ በእግዚአብሔር ፡ አድናቸዋለኹ ፡ እንጂ ፡ በቀስት ፡
ወይም ፡ በሰይፍ ፡ ወይም ፡ በሰልፍ ፡ ወይም ፡ በፈረሶች ፡ ወይም ፡ በፈረሰኞዎች ፡ አላድናቸውም ፡ አለው ።

8 ፤ ሎሩሃማም ፡ ጡት ፡ ባስጣለች ፡ ጊዜ ፥ ደግሞ ፡ ፀነሰች ፡ ወንድ ፡ ልጅንም ፡ ወለደች ።

9 ፤ እግዚአብሔርም ፦ ሕዝቤ ፡ አይደላችኹምና ፥ እኔም ፡ አምላክ ፡ አልኾናችኹምና ፡ ስሙን ፡ ሎዓሚ ፡ ብለኽ ፡
ጥራው ፡ አለው ።

ትንቢተ ፡ ሆሴዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 2 ።

ምዕራፍ ፡ 2 ።

1 ፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ቍጥር ፡ እንደማይሰፈርና ፡ እንደማይቈጠር ፡ እንደ ፡ ባሕር ፡ አሸዋ ፡ ይኾናል ፤ እንዲህም ፡
ይኾናል ፤ እናንተ ፡ ሕዝቤ ፡ አይደላችኹም ፡ ተብሎ ፡ በተነገረበት ፡ በዚያ ፡ ስፍራ ፡ የሕያው ፡ አምላክ ፡ ልጆች ፡ ይባላሉ ።

2 ፤ የይሁዳ ፡ ልጆችና ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በአንድነት ፡ ይሰበሰባሉ ፥ ለእነርሱም ፡ አንድ ፡ አለቃ ፡
ይሾማሉ ፥ ከምድሪቱም ፡ ይወጣሉ ፤ የኢይዝራኤል ፡ ቀን ፡ ታላቅ ፡ ይኾናልና ።

3 ፤ ወንድሞቻችኹን ፦ ዓሚ ፥ እኅቶቻችኹንም ፦ ሩሃማ ፡ በሏቸው ።

4 ፤ እናታችኹ ፡ ሚስቴ ፡ አይደለችምና ፥ እኔም ፡ ባሏ ፡ አይደለኹምና ፡ ተሟገቱ ፤ ከእናታችኹ ፡ ጋራ ፡
ተሟገቱ ። ግልሙትናዋን ፡ ከፊቷ ፥ ምንዝርናዋንም ፡ ከጡቶቿ ፡ መካከል ፡ ታስወግድ ፤

5 ፤ ዕራቍቷን ፡ እንዳልገፋት ፥ እንደተወለደችበትም ፡ ቀን ፡ እንዳላደርጋት ፥ እንደ ፡ ምድረ ፡ በዳና ፡ እንደ ፡ ደረቅ ፡
ምድር ፡ እንዳላደርጋት ፥ በጥማትም ፡ እንዳልገድላት ፤

6 ፤ የግልሙትናዋ ፡ ልጆች ፡ ናቸውና ፥ ልጆቿን ፡ አልምርም ።

7 ፤ እናታቸው ፡ አመንዝራለች ፤ የፀነሰቻቸውም ፦ እንጀራዬንና ፡ ውሃዬን ፥ ጥጤንና ፡ የተልባ ፡ እግሬን ፥ ዘይቴንና ፡
መጠጤን ፡ ከሚሰጡኝ ፡ ከውሽማዎቼ ፡ በዃላ ፡ እኼዳለኹ ፡ ብላ ፡ አስነወረቻቸው ።

8 ፤ ስለዚህ ፥ እንሆ ፥ መንገድሽን ፡ በሾኽ ፡ እዘጋለኹ ፥ መንገዷንም ፡ እንዳታገኝ ፡ ቅጥርን ፡ እቀጥርባታለኹ ።

9 ፤ ውሽማዎቿንም ፡ ትከተላለች ፥ ነገር ፡ ግን ፥ አትደርስባቸውም ፤ ትፈልጋቸውማለች ፥ ነገር ፡
ግን ፥ አታገኛቸውም ፤ ርሷም ፡— ከዛሬ ፡ ይልቅ ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ይሻለኝ ፡ ነበርና ፥ ተመልሼ ፡ ወደቀደመው ፡ ባሌ ፡
እኼዳለኹ ፡ ትላለች ።

10 ፤ ርሷም ፡ እኽልንና ፡ ወይንን ፡ ጠጅ ፡ ዘይትንም ፡ የሰጠኋት ፥ ለበዓልም ፡ የተሠራውን ፡ ብርና ፡ ወርቅ ፡ ያበዛኹላት ፡
እኔ ፡ እንደ ፡ ኾንኹ ፡ አላወቀችም ።

11 ፤ ስለዚህ ፥ እኽሌን ፡ በጊዜዋ ፥ ወይን ፡ ጠጄንም ፡ በወረቷ ፡ እወስዳለኹ ፥ ዕራቍትነቷንም ፡ እንዳትሸፍን ፡ ጥጤንና ፡
የተልባ ፡ እግሬን ፡ እገፋታለኹ ።

12 ፤ አኹንም ፡ ውሽማዎቿ ፡ እያዩ ፡ ነውሯን ፡ እገልጣለኹ ፤ ከእጄም ፡ ማንም ፡ አያድናትም ።

13 ፤ ደስታዋንም ፡ ኹሉ ፥ በዓላቷንም ፥ መባቻዎቿንም ፥ ሰንበቶቿንም ፥ የተቀደሱትንም ፡ ጉባኤዎችን ፡ ኹሉ ፡
አስቀራለኹ ።

14 ፤ ርሷም ፡— ውሽማዎቼ ፡ የሰጡኝ ፡ ዋጋዬ ፡ ይህ ፡ ነው ፡ ያለችውን ፡ ወይኗንና ፡ በለሷን ፡ አጠፋለኹ ፤ ዱርም ፡
አደርገዋለኹ ፥ የምድረ ፡ በዳም ፡ አራዊት ፡ ይበሉታል ።

15 ፤ እኔን ፡ ረስታ ፡ ውሽማዎቿን ፡ እየተከተለች ፥ በጕትቾቿና ፡ በጌጧም ፡ እያጌጠች ፡ ለበዓሊም ፡ ያጠነችበትን ፡
ወራት ፡ እበቀልባታለኹ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

16 ፤ ስለዚህ ፥ እንሆ ፥ አባብላታለኹ ፥ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳም ፡ አመጣታለኹ ፥ ለልቧም ፡ እናገራለኹ ።

17 ፤ ከዚያም ፡ የወይን ፡ ቦታዋን ፥ የተስፋ ፡ በርም ፡ እንዲኾንላት ፡ የዐኮርን ፡ ሸለቆ ፡ እሰጣታለኹ ፤ በዚያም ፡ ከግብጽ ፡
ምድር ፡ እንደ ፡ ወጣችበት ፡ ቀን ፡ እንደ ፡ ሕፃንነቷ ፡ ወራት ፡ ትዘምራለች ።

18 ፤ በዚያ ፡ ቀን ፡ ባሌ ፡ ብለሽ ፡ ትጠሪኛለሽ ፡ እንጂ ፡ ዳግመኛ ፡ በኣሌ ፡ ብለሽ ፡ አትጠሪኝም ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤

19 ፤ የበዓሊምን ፡ ስም ፡ ከአፏ ፡ አስወግደዋለኹና ፥ በስማቸውም ፡ እንግዲህ ፡ አይታሰቡምና ።

20 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ ከምድር ፡ አራዊትና ፡ ከሰማይ ፡ ወፎች ፡ ከመሬትም ፡ ተንቀሳቃሾች ፡ ጋራ ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡
አደርግላቸዋለኹ ፤ ቀስትንና ፡ ሰይፍን ፡ ሰልፍንም ፡ ከምድሩ ፡ እሰብራለኹ ፥ ተከልለውም ፡ እንዲኖሩ ፡ አስተኛቸዋለኹ ።

21 ፤ ለዘለዓለምም ፡ ለእኔ ፡ እንድትኾኚ ፡ ዐጭሻለኹ ፤ በጽድቅና ፡ በፍርድ ፡ በምሕረትና ፡ በርኅራኄ ፡ ዐጭሻለኹ ።

22 ፤ ለኔም ፡ እንድትኾኚ ፡ በመታመን ፡ ዐጭሻለኹ ፤ አንቺም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ታውቂያለሽ ።

23 ፤ በዚያንም ፡ ቀን ፡ እመልሳለኹ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ ለሰማይ ፡ እመልሳለኹ ፥ ሰማይም ፡ ለምድር ፡ ይመልሳል ፤

24 ፤ ምድርም ፡ ለእኽልና ፡ ለወይን ፡ ጠጅ ፡ ለዘይትም ፡ ትመልሳለች ፤ እነርሱም ፡ ለኢይዝራኤል ፡ ይመልሳሉ ።

25 ፤ በምድርም ፡ ላይ ፡ ለእኔ ፡ እዘራታለኹ ፤ ምሕረትም ፡ የሌላትን ፡ እምራለኹ ፥ ሕዝቤም ፡ ያልኾነውን ፡— አንተ ፡
ሕዝቤ ፡ ነኽ ፡ እለዋለኹ ፤ ርሱም ፡— አንተ ፡ አምላኬ ፡ ነኽ ፡ ይለኛል ።

ትንቢተ ፡ ሆሴዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 3 ።

ምዕራፍ ፡ 3 ።

1 ፤ እግዚአብሔርም ፡— የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ ሌላዎች ፡ አማልክት ፡ ቢመለሱና ፡ የዘቢብ ፡ ጥፍጥፍን ፡ ቢወዱ ፡
እንኳ ፥ እግዚአብሔር ፡ እንደሚወዳቸው ፡ አንተም ፡ ውሽማዋን ፡ የምትወደውን ፡ አመንዝራዪትን ፡ ሴት ፡ ውደድ ፡
አለኝ ።

2 ፤ እኔም ፡ በዐሥራ ፡ ዐምስት ፡ ብርና ፡ ባንድ ፡ ቆሮስ ፡ መስፈሪያ ፡ ተኩል ፡ ገብስ ፡ ገዛኋት ።

3 ፤ ከእኔ ፡ ጋራ ፡ ብዙ ፡ ወራት ፡ ተቀመጪ ፥ አታመንዝሪም ፥ ለሌላ ፡ ሰውም ፡ አትኹኚ ፤ እኔም ፡ እንዲሁ ፡
እኾንልሻለኹ ፡ አልኋት ።

4 ፤ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ያለንጉሥና ፡ ያለአለቃ ፥ ያለመሥዋዕትና ፡ ያለዐምድ ፥ ያለኤፉድና ፡ ያለተራፊም ፡ ብዙ ፡
ወራት ፡ ይቀመጣሉና ፤

5 ፤ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ተመልሰው ፡ አምላካቸውን ፡ እግዚአብሔርንና ፡ ንጉሣቸውን ፡ ዳዊትን ፡ ይፈልጋሉ ፤ በኋለኛውም ፡ ዘመን ፡ ፈርተው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔርና ፡ ወደ ፡ በረከቱ ፡ ይመጣሉ ።

ትንቢተ ፡ ሆሴዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 4 ።

ምዕራፍ ፡ 4 ።

1 ፤ እናንተ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፥ እውነትና ፡ ምሕረት ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ማወቅ ፡ በምድር ፡ ስለሌለ ፡ እግዚአብሔር ፡ በምድሩ ፡ ላይ ፡ ከሚኖሩ ፡ ጋራ ፡ ክርክር ፡ አለውና ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስሙ ።

2 ፤ ርግማንና ፡ ሐሰት ፡ ግዳይና ፡ ስርቆት ፡ ምንዝርናም ፡ ወጥተዋል ፤ ደምም ፡ ወደ ፡ ደም ፡ ደርሷል ።

3 ፤ ስለዚህ ፥ ምድሪቱ ፡ ታለቅሳለች ፥ በርሷም ፡ የሚቀመጡ ፡ ኹሉ ፡ ከምድር ፡ አራዊትና ፡ ከሰማይ ፡ ወፎች ፡ ጋራ ፡ ይደክማሉ ፤ የባሕሩም ፡ ዓሣዎች ፡ ያልቃሉ ።

4 ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ሕዝብኽ ፡ ከካህን ፡ ጋራ ፡ እንደሚከራከሩ ፡ ናቸውና ፥ ማንም ፡ አይከራከር ፥ ማንም ፡ አይዝለፍ ።

5 ፤ በቀንም ፡ ትሰናከላለኽ ፥ ነቢዩም ፡ ከአንተ ፡ ጋራ ፡ በሌሊት ፡ ይሰናከላል ፤ እናትኽንም ፡ አጠፋታለኹ ።

6 ፤ ሕዝቤ ፡ ዕውቀት ፡ ከማጣቱ ፡ የተነሣ ፡ ጠፍቷል ፤ አንተም ፡ ዕውቀትን ፡ ጠልተኻልና ፥ እኔ ፡ ካህን ፡ እንዳትኾነኝ ፡ እጠላኻለኹ ፤ የአምላክኽንም ፡ ሕግ ፡ ረስተኻልና ፥ እኔ ፡ ደግሞ ፡ ልጆችኽን ፡ እረሳለኹ ።

7 ፤ እንደ ፡ ብዛታቸው ፡ መጠን ፡ ኀጢአት ፡ ሠሩብኝ ፤ እኔም ፡ ክብራቸውን ፡ ወደ ፡ ነውር ፡ እለውጣለኹ ።

8 ፤ የሕዝቤም ፡ ኀጢአት ፡ መብል ፡ ኾኖላቸዋል ፥ ልባቸውንም ፡ ወደ ፡ በደላቸው ፡ አድርገዋል ።

9 ፤ እንደ ፡ ሕዝቡም ፡ እንዲሁ ፡ ካህኑ ፡ ይኾናል ፤ በመንገዳቸውም ፡ እበቀላቸዋለኹ ፥ ሥራቸውንም ፡ እመልስባቸዋለኹ ።

10 ፤ እግዚአብሔርንም ፡ መጠበቅ ፡ ትተዋልና ፥ ሲበሉ ፡ አይጠግቡም ፥ ሲያመነዝሩም ፡ አይበዙም ።

11 ፤ ግልሙትናና ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ስካርም ፡ አእምሮን ፡ ያጠፋል ።

12 ፤ የግልሙትና ፡ መንፈስ ፡ ሕዝቤን ፡ አስቷቸዋልና ፥ እነርሱም ፡ ከአምላካቸው ፡ ርቀው ፡ አመንዝረዋልና ፥ በትራቸውን ፡ ይጠይቃሉ ፥ ዘንጋቸውም ፡ ይመልስላቸዋል ።

13 ፤ በተራራዎችም ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ይሠዋሉ ፤ ጥላውም ፡ መልካም ፡ ነውና ፥ ከኮምበልና ፡ ከልብን ፤ ከአሆማም ፡ ዛፍ ፡ በታች ፡ በኰረብታዎች ፡ ላይ ፡ ያጥናሉ ፤ ስለዚህ ፥ ሴቶች ፡ ልጆቻችኹ ፡ ይገለሙታሉ ፥ ሙሽሮቻችኹም ፡ ያመነዝራሉ ።

14 ፤ ወንዶችም ፡ ደግሞ ፡ ከጋለሞታዎች ፡ ጋራ ፡ ይጫወታሉና ፥ ከጋለሞታዎችም ፡ ጋራ ፡ ይሠዋሉና ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻችኹ ፡ በገለሞቱ ፡ ጊዜ ፥ ሙሽሮቻችኹም ፡ ባመነዘሩ ፡ ጊዜ ፡ አልቀጣቸውም ፤ የማያስተውልም ፡ ሕዝብ ፡ ይገለበጣል ።

15 ፤ እስራኤል ፡ ሆይ ፥ አንተ ፡ ብታመነዝር ፡ ይሁዳ ፡ አይበድል ፤ እናንተም ፡ ወደ ፡ ገልገላ ፡ አትግቡ ፥ ወደ ፡ ቤትአዌንም ፡ አትውጡ ፥ ወይም ፦ ሕያው ፡ እግዚአብሔርን! ብላችኹ ፡ አትማሉ ።

16 ፤ እስራኤል ፡ እንደ ፡ እልከኛ ፡ ጊደር ፡ እንቢ ፡ ብሏል ፤ እግዚአብሔርስ ፡ በሰፊው ፡ ቦታ ፡ እንደ ፡ ጠቦት ፡ ያሰማራዋልን ፧

17 ፤ ኤፍሬም ፡ ከጣዖታት ፡ ጋራ ፡ ተጋጠመ ፤ ተወው ።

18 ፤ ስካርን ፡ ፈጽመዋል ፥ ግልሙትናንም ፡ አብዝተዋል ፤ አለቃዎቿም ፡ ነውርን ፡ እጅግ ፡ ወደዱ ።

19 ፤ ነፋስ ፡ በክንፏ ፡ አስሯታል ፤ ከመሥዋዕታቸውም ፡ የተነሣ ፡ ያፍራሉ ።

ትንቢተ ፡ ሆሴዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 5 ።

ምዕራፍ ፡ 5 ።

1 ፤ ካህናት ፡ ሆይ ፥ ይህን ፡ ስሙ ፤ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ፥ አድምጡ ፤ የንጉሥ ፡ ቤት ፡ ሆይ ፥ ልብ ፡

አድርጉ ፤ በምጽጳ ፡ ላይ ፡ ወጥመድ ፥ በታቦርም ፡ ላይ ፡ የተዘረጋ ፡ አሽክላ ፡ ኾናችኋልና ፥ ፍርድ ፡ በእናንተ ፡ ላይ ፡ ነው ።

2 ፤ ዐመፀኛዎችም ፡ ዕርድ ፡ አብዝተዋል ፤ እኔ ፡ ግን ፡ እነዚያን ፡ ኹሉ ፡ እዘልፋለኹ ።

3 ፤ ኤፍሬምን ፡ ዐውቀዋለኹ ፥ እስራኤልም ፡ ከእኔ ፡ አልተሰወረም ፤ ኤፍሬም ፡ ሆይ ፥ ዛሬ ፡ አመንዝረኻል ፥ እስራኤልም ፡ ረክሷል ።

4 ፤ ወደ ፡ አምላካቸው ፡ ይመለሱ ፡ ዘንድ ፡ ሥራቸውን ፡ አላቀኑም ፤ የግልሙትና ፡ መንፈስ ፡ በውስጣቸው ፡ አለና ፤ እግዚአብሔርንም ፡ አላወቁምና ።

5 ፤ የእስራኤልም ፡ ትዕቢት ፡ በፊቱ ፡ ይመሰክራል ፤ ስለዚህ ፥ እስራኤልና ፡ ኤፍሬም ፡ በኀጢአታቸው ፡ ይሰናከላሉ ፤ ይሁዳም ፡ ደግሞ ፡ ከነሱ ፡ ጋራ ፡ ይሰናከላል ።

6 ፤ እግዚአብሔርንም ፡ ለመሻት ፡ በጎቻቸውንና ፡ ላሞቻቸውን ፡ ነድተው ፡ ይኼዳሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ርሱ ፡ ከነርሱም ፡ ተመልሷልና ፥ አያገኙትም ።

7 ፤ ዲቃላዎችን ፡ ልጆች ፡ ወልደዋልና ፥ እግዚአብሔርን ፡ ወንጅለዋል ፤ አኹንም ፡ አንድ ፡ ወር ፡ እነርሱንና ፡ ርስታቸውን ፡ ይበላቸዋል ።

8 ፤ በጊብዓ ፡ መለከትን ፥ በራማ ፡ እንቢልታን ፡ ንፉና ፦ ብንያም ፡ ሆይ ፥ ከአንተ ፡ በኋላ ፥ እያላችኹ ፡ በቤትአዌን ፡ ላይ ፡ እሪ ፡ በሉ ።

9 ፤ ኤፍሬም ፡ በዘለፋ ፡ ቀን ፡ የፈረሰ ፡ ይኾናል ። በእስራኤል ፡ ነገዶች ፡ ዘንድ ፡ በርግጥ ፡ የሚኾነውን ፡ ነገር ፡ ገልጫለኹ ።

10 ፤ የይሁዳ ፡ አለቃዎች ፡ ድንበርን ፡ እንደሚነቅሉ ፡ ኾነዋል ፤ እኔም ፡ መዓቴን ፡ እንደ ፡ ውሃ ፡ አፈስባቸዋለኹ ።

11 ፤ ኤፍሬም ፡ ከትእዛዝ ፡ በኋላ ፡ መኼድን ፡ ወዷልና ፥ የተገፋና ፡ በፍርድ ፡ የተጐዳ ፡ ኾኗል ።

12 ፤ እኔም ፡ ለኤፍሬም ፡ እንደ ፡ ብል ፥ ለይሁዳም ፡ ቤት ፡ እንደ ፡ ነቀዝ ፡ ኾኛለኹ ።

13 ፤ ኤፍሬምም ፡ ደዌውን ፥ ይሁዳም ፡ ቍስሉን ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ኤፍሬም ፡ ወደ ፡ አሶር ፡ ኼደ ፡ ወደ ፡ ንጉሡም ፡ ወደ ፡ ኢያሪም ፡ መልእክተኛን ፡ ላከ ፤ ርሱ ፡ ግን ፡ ይፈውሳችኹ ፡ ዘንድ ፥ ከቍስላችኹም ፡ ያድናችኹ ፡ ዘንድ ፡ አልቻለም ።

14 ፤ እኔም ፡ ለኤፍሬም ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፥ ለይሁዳም ፡ ቤት ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ደቦል ፡ እኾናለኹና ፤ እኔም ፡ ነጥቄ ፡ እኼዳለኹ ፡ እወስድማለኹ ፥ የሚያድንም ፡ አይገኝም ።

15 ፤ በደላቸውንም ፡ እስኪያውቁ ፡ ድረስ ፥ ፊቴንም ፡ እስኪሹ ፡ ድረስ ፡ ኼጄ ፡ ወደ ፡ ስፍራዬ ፡ እመለሳለኹ ፤ በመከራቸው ፡ ጊዜ ፡ እጅግ ፡ አድርገው ፡ ፊቴን ፡ ይፈልጋሉ ።

ትንቢተ ፡ ሆሴዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 6 ።

ምዕራፍ ፡ 6 ።

1 ፤ ኑ ፥ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንመለስ ፤ ርሱ ፡ ሰብሮናልና ፥ ርሱም ፡ ይፈውሰናል ፤ ርሱ ፡ መቶናል ፥ ርሱም ፡ ይጠግነናል ።

2 ፤ ከኹለት ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ያድነናል ፤ በሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ ያስነሣናል ፥ በፊቱም ፡ በሕይወት ፡ እንኖራለን ።

3 ፤ እንወቅ ፤ እናውቀውም ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንከተል ፤ እንደ ፡ ወገግታም ፡ ተዘጋጅቶ ፡ እናገኘዋለን ፤ እንደ ፡ ዝናብም ፡ ምድርንም ፡ እንደሚያጠጣ ፡ እንደ ፡ መጨረሻ ፡ ዝናብ ፡ ይመጣል ።

4 ፤ ምሕረታችኹ ፡ እንደ ፡ ማለዳ ፡ ደመና ፥ በማለዳም ፡ እንደሚያልፍ ፡ ጠል ፡ ነውና ፥ ኤፍሬም ፡ ሆይ ፥ ምን ፡ ላድርግልኽ ፤ ይሁዳ ፡ ሆይ ፥ ምን ፡ ላድርግልኽ ፤

5 ፤ ስለዚህ ፥ በነቢያት ፡ እጅ ፡ ቈረጥኋቸው ፥ በአፌም ፡ ቃል ፡ ገደልኋቸው ፤ ፍርዴም ፡ እንደ ፡ ብርሃን ፡ ይወጣል ።

6 ፤ ከመሥዋዕት ፡ ይልቅ ፡ ምሕረትን ፥ ከሚቃጠልም ፡ መሥዋዕት ፡ ይልቅ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ማወቅ ፡ እወዳለኹና ።

7 ፤ እነርሱ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ አዳም ፡ ቃል ፡ ኪዳንን ፡ ተላልፈዋል ፤ በዚያም ፡ ላይ ፡ ወንጅለውኛል ።

8 ፤ ገለዓድ ፡ ኀጢአትን ፡ የሚሠሩ ፡ ሰዎች ፡ ከተማ ፥ በደምም ፡ የተቀባ ፡ ነው ።

9 ፤ ለሰውም ፡ እንደሚያደቡ ፡ ወንበዴዎች ፥ እንዲሁ ፡ የካህናት ፡ ወገኖች ፡ በሴኬም ፡ መንገድ ፡ ላይ ፡
ይገድላሉ ፤ ሴሰኝነትንም ፡ ያደርጋሉ ።

10 ፤ በእስራኤል ፡ ቤት ፡ የሚያስፈራን ፡ ነገር ፡ አይቻለኹ ፤ በዚያ ፡ በኤፍሬም ፡ ውስጥ ፡ ግልሙትና ፡
ተገኘ ፥ እስራኤልም ፡ ረክሷል ።

11 ፤ ይሁዳ ፡ ሆይ ፥ የሕዝቤን ፡ ምርኮ ፡ በምመልስበት ፡ ጊዜ ፡ ለአንተ ፡ ደግሞ ፡ መከር ፡ ተወስኖልኻል ።

ትንቢተ ፡ ሆሴዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 7 ።

ምዕራፍ ፡ 7 ።

1 ፤ በሐሰት ፡ አድርገዋልና ፥ ሌባም ፡ ገብቷልና ፥ በውጭም ፡ ወንበዴዎች ፡ ቀምተዋልና ፥ እስራኤልን ፡ እፈውስ ፡ ዘንድ ፡
በወደድኹ ፡ ጊዜ ፡ የኤፍሬም ፡ ኀጢአትና ፡ የሰማርያ ፡ ክፋት ፡ ተገለጠ ።

2 ፤ እኔም ፡ ክፋታቸውን ፡ ዅሉ ፡ እንዳሰብኹ ፡ በልባቸው ፡ አያስቡም ፡ አኹንም ፡ ሥራቸው ፡ ከበባቸዋለች ፥ በፊቴም ፡
አለች ።

3 ፤ ንጉሡን ፡ በክፋታቸው ፥ አለቃዎቹንም ፡ በሐሰታቸው ፡ ደስ ፡ አሰኝተዋል ።

4 ፤ ዅሉም ፡ አመንዝራዎች ፡ ናቸው ፤ ጋጋሪ ፡ እንደሚያነድበት ፡ እንደ ፡ ምድጃ ፡ ናቸው ፤ ዅሉ ፡ እስኪቦካ ፡ ድረስ ፡
እሳትን ፡ መቈስቈስና ፡ ርሾን ፡ መለወስ ፡ ይቈያል ።

5 ፤ በንጉሣችን ፡ ቀን ፡ አለቃዎች ፡ ከወይን ፡ ጠጅ ፡ ሙቀት ፡ የተነሣ ፡ ታመሙ ፤ ርሱም ፡ ከዋዘኛዎች ፡ ጋራ ፡ እጁን ፡
ዘረጋ ።

6 ፤ እያደቡ ፡ ልባቸውን ፡ እንደ ፡ ምድጃ ፡ አዘጋጅተዋል ፤ አበዛቸውም ፡ ሌሊቱን ፡ ዅሉ ፡ አንቀላፋ ፤ በጠባም ፡ ጊዜ ፡
እንደ ፡ እሳት ፡ ነበልባል ፡ ይነዳል ።

7 ፤ ዅሉም ፡ እንደ ፡ ምድጃ ፡ ግለዋል ፥ ፈራጆቻቸውንም ፡ በሉ ፤ ነገሥታታቸውም ፡ ዅሉ ፡ ወደቁ ፤ ከነርሱም ፡ ወደ ፡
እኔ ፡ የሚጮኽ ፡ የለም ።

8 ፤ ኤፍሬም ፡ ከአሕዛብ ፡ ጋራ ፡ ተደባለቀ ፤ ኤፍሬም ፡ እንዳልተገላበጠ ፡ ቂጣ ፡ ነው ።

9 ፤ እንግዳዎች ፡ ጕልበቱን ፡ በሉት ፥ ርሱም ፡ አላወቀም ፤ ሽበትም ፡ ወጣበት ፥ ርሱም ፡ አላወቀም ።

10 ፤ የእስራኤልም ፡ ትዕቢቱ ፡ በፊቱ ፡ መሰከረ ፤ ወደ ፡ አምላካቸው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡
አልተመለሱም ፥ በዚህም ፡ ዅሉ ፡ አልፈለጉትም ።

11 ፤ ኤፍሬምም ፡ አእምሮ ፡ እንደሌላት ፡ እንደ ፡ ሰነፍ ፡ ርግብ ፡ ነው ፤ ግብጽን ፡ ጠሩ ፥ ወደ ፡ አሶርም ፡ ኼዱ ።

12 ፤ ሲኼዱ ፡ አሽክላዬን ፡ እዘረጋባቸዋለኹ ፤ እንደሰማይ ፡ ወፎች ፡ አወርዳቸዋለኹ ፤ መከራቸውን ፡ ሲሰሙ ፡
እገሥጻቸዋለኹ ።

13 ፤ ከእኔ ፡ ፈቀቅ ፡ ብለዋልና ፥ ወዮላቸው! በእኔም ፡ ላይ ፡ ዐምፀዋልና ፥ ጥፋት ፡ ይምጣባቸው! እኔ ፡ ልታደጋቸው ፡
ወደድኹ ፥ እነርሱ ፡ ግን ፡ በሐሰት ፡ ተናገሩብኝ ።

14 ፤ በመኝታቸው ፡ ላይ ፡ ኾነው ፡ ያለቅሱ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ በልባቸው ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አልጮኹም ፤ ስለ ፡ እኽልና ፡ ስለ ፡
ወይን ፡ ጠጅ ፡ ይሰበሰቡ ፡ ነበር ፤ በእኔም ፡ ላይ ፡ ዐመፁ ።

15 ፤ እኔም ፡ ክንዳቸውን ፡ አስተማርኹና ፡ አጸናኹ ፤ እነርሱ ፡ ግን ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡ መከሩብኝ ።

16 ፤ ወደ ፡ ከንቱ ፡ ነገር ፡ ተመለሱ ፤ እንደ ፡ ተንኰለኛ ፡ ቀስት ፡ ኾኑ ፤ አለቃዎቻቸው ፡ ከምላሳቸው ፡ ቍጣ ፡ የተነሣ ፡
በሰይፍ ፡ ይወድቃሉ ፤ ይህ ፡ በግብጽ ፡ ምድር ፡ ውስጥ ፡ መሳለቂያ ፡ ይኾንባቸዋል ።

ትንቢተ ፡ ሆሴዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 8 ።

ምዕራፍ ፡ 8 ።

1 ፤ መለከትን ፡ ወደ ፡ አፍኽ ፡ አቅርብ ፤ ቃል ፡ ኪዳኔን ፡ ተላልፈዋልና ፥ በሕጌም ፡ ላይ ፡ ዐምፀዋልና ፥ በእግዚአብሔር ፡
ቤት ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ንስር ፡ ይመጣል ።

2 ፤ እነርሱም ፦ አምላክ ፡ ሆይ ፥ እኛ ፡ እስራኤል ፡ ዐወቅንኽ ፡ ብለው ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ይጮኻሉ ።

3 ፤ እስራኤል ፡ ደግነትን ፡ ጥሏል ፤ ጠላትም ፡ ያሳድዱታል ።

4 ፤ ለራሳቸው ፡ ነገሥታትን ፡ አነገሡ ፥ ከእኔም ፡ ዘንድ ፡ አይደለም ፤ አለቃዎችንም ፡ አደረጉ ፥ እኔም ፡
አላወቅኹም ፤ ለጥፋታቸውም ፡ ከብራቸውና ፡ ከወርቃቸው ፤ ጣዖታትን ፡ ለራሳቸው ፡ አደረጉ ።

5 ፤ ሰማርያ ፡ ሆይ ፥ እንቦሳኽን ፤ ጥሏል ፤ ቍጣዬ ፡ በላያቸው ፡ ነዷል ፤ እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ ንጹሕ ፡ ሊኾኑ ፡
አይችሉም ፧

6 ፤ ይህ ፡ ደግሞ ፡ ከእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ነው ፤ ሠራተኛ ፡ ሠራው ፥ ርሱም ፡ አምላክ ፡ አይደለም ፤ የሰማርያም ፡ እንቦሳ ፡
ይቈራረጣል ።

7 ፤ ነፋስን ፡ ዘርተዋል ፥ ዐውሎ ፡ ነፋስንም ፡ ያጭዳሉ ፤ አገዳ ፡ የለውም ፥ ከፍሬውም ፡ ዱቄት ፡ አይገኝም ፤ ቢገኝም ፡
እንግዳዎች ፡ ይበሉታል ።

8 ፤ እስራኤል ፡ ተውጧል ፥ በአሕዛብም ፡ መካከል ፡ ዛሬ ፡ እንደ ፡ ረከሰ ፡ ዕቃ ፡ ኾኗል ።

9 ፤ ለብቻውም ፡ እንደሚቀመጥ ፡ እንደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ አህያ ፡ ወደ ፡ አሶር ፡ ወጥተዋል ፤ ኤፍሬምም ፡ ወዳጆቹን ፡
በእጅ ፡ መንሻ ፡ ገዛ ።

10 ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ለአሕዛብ ፡ እጅ ፡ መንሻ ፡ ቢሰጡ ፡ እኔ ፡ አኹን ፡ እሰበስባቸዋለኹ ፤ ከንጉሥና ፡ ከአለቃዎችም ፡
ሸክም ፡ የተነሣ ፡ ይደክማሉ ።

11 ፤ ኤፍሬም ፡ ኀጢአትን ፡ ለመሥራት ፡ መሠዊያ ፡ አብዝቷልና ፥ መሠዊያ ፡ ለኀጢአት ፡ ይኾንለታል ።

12 ፤ የሕጌን ፡ ብዛት ፡ጽፌለታለኹ ፤ እነርሱ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ እንግዳ ፡ ነገር ፡ ቈጥረውታል ።

13 ፤ መሥዋዕቴን ፡ ያቀርባሉ ፥ ሥጋንም ፡ ያርዳሉ ፥ ይበላሉም ፤ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ አይቀበላቸውም ፤ በደላቸውንም ፡
ያስባል ፥ ኀጢአታቸውንም ፡ ይቀጣል ፤ እነርሱም ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ ይመለሳሉ ።

14 ፤ እስራኤል ፡ ፈጣሪውን ፡ ረስቷል ፥ መስገጃዎችንም ፡ ሠርቷል ፤ ይሁዳም ፡ የተመሸጉትን ፡ ከተማዎች ፡
አብዝቷል ፤ እኔ ፡ ግን ፡ በከተማዎች ፡ ላይ ፡ እሳትን ፡ እሰዳለኹ ፥ አዳራሾችንም ፡ ትበላለች ።

__________________ትንቢተ ፡ ሆሴዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 9 ። __________________

ምዕራፍ ፡ 9 ።

1 ፤ እስራኤል ፡ ሆይ ፥ ከአምላክኽ ፡ ተለይተኽ ፡ አመንዝረኻልና ፥ እንደ ፡ አሕዛብ ፡ ደስ ፡ አይበልኽ ፥ ሐሴትንም ፡
አታድርግ ፤ በእኽሉ ፡ ዐውድማ ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፡ የግልሙትናን ፡ ዋጋ ፡ ወደኻል ።

2 ፤ ዐውድማውና ፡ መጥመቂያው ፡ አይመግባቸውም ፥ ጕሽ ፡ ጠጅም ፡ ይጐድልባታል ።

3 ፤ በእግዚአብሔር ፡ ምድር ፡ ላይ ፡ አይቀመጡም ፤ ኤፍሬምም ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ ይመለሳል ፥ በአሶርም ፡ ርኩስን ፡ ነገር ፡
ይበላሉ ።

4 ፤ ለእግዚአብሔርም ፡ የወይን ፡ ጠጅን ፡ ቍርባን ፡ አያፈሱም ፥ መሥዋዕታቸውም ፡ ደስ ፡ አያሠኘውም ፤ የሐዘንም ፡
እንጀራ ፡ ይኾንላቸዋል ፥ የሚበላውም ፡ ኹሉ ፡ ይረክሳል ፤ እንጀራቸውም ፡ ለሰውነታቸው ፡ ይኾናል ፡ እንጂ ፡
ወደእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ አይገባም ።

5 ፤ በዓመት ፡ በዓል ፡ ቀንና ፡ በእግዚአብሔር ፡ በዓል ፡ ቀን ፡ ምን ፡ ታደርጋላችኹ ፧

6 ፤ እንሆ ፥ ከጥፋት ፡ ሸሽተው ፡ ኼዱ ፥ ግብጽም ፡ ትሰበስባቸዋለች ፥ ሜምፎስም ፡ ትቀብራቸዋለች ፤ ሳማም ፡
የብራቸውን ፡ ጌጥ ፡ ይወርሳል ፥ ሾኽም ፡ በድንኳኖቻቸው ፡ ውስጥ ፡ ይበቅላል ።

7 ፤ የበቀል ፡ ወራት ፡ መጥቷል ፥ የፍዳም ፡ ወራት ፡ ደርሷል ፥ እስራኤልም ፡ ያውቃል ፤ ከኀጢአትኽና ፡ ከጠላትነትኽ ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ ነቢዩ ፡ ሰንፏል ፥ መንፈስም ፡ ያለበት ፡ ሰው ፡ አብዷል ።

8 ፤ ኤፍሬም ፡ ከአምላኬ ፡ ጋራ ፡ ተመልካች ፡ ነበረ ፤ አኹን ፡ ግን ፡ ነቢዩ ፡ በመንገዱ ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፡ የወፍ ፡ ወጥመድ ፡ ኾነ ፥ በአምላኩም ፡ ቤት ፡ ጠላትነት ፡ አለ ።

9 ፤ በጊብዓ ፡ ዘመን ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ እጅግ ፡ ረከሱ ፤ ርሱም ፡ በደላቸውን ፡ ያስባል ፥ ኀጢአታቸውንም ፡ ይበቀላል ።

10 ፤ እስራኤልን ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ እንዳለ ፡ ወይን ፡ ኾኖ ፡ አገኘኹት ፤ አባቶቻችኹንም ፡ ከመዠመሪያዋ ፡ ዓመት ፡ እንደ ፡ በለስ ፡ በኵራት ፡ ኾነው ፡ አየኋቸው ፤ እነርሱ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ብዔልፌጎር ፡ መጡ ፥ ለነውርም ፡ ተለዩ ፥ እንደ ፡ ወደዱትም ፡ ርኩስ ፡ ኾኑ ፥

11 ፤ የኤፍሬምም ፡ ክብር ፡ እንደ ፡ ወፍ ፡ በሮ ፡ ይጠፋል ፤ መውለድና ፡ መፅነስ ፡ ማርገዝም ፡ አይኾንላቸውም ።

12 ፤ ልጆቻቸውንም ፡ ቢያሳድጉ ፡ ሰው ፡ እንዳይቀርላቸው ፡ ልጅ ፡ አልባ ፡ አደርጋቸዋለኹ ፤ ከነርሱም ፡ በራቅኹ ፡ ጊዜ ፡ ወዮላቸው!

13 ፤ እኔ ፡ እንዳየኹ ፡ የኤፍሬም ፡ ልጆች ፡ ለምርኮ ፡ ተሰጥተዋል ፤ ኤፍሬምም ፡ ልጆቹን ፡ ወደ ፡ ገዳዮች ፡ ያወጣል ።

14 ፤ አቤቱ ፥ ስጣቸው ፤ ምን ፡ ትሰጣቸዋለኽ ፧ የሚጨነግፍን ፡ ማሕፀን ፡ የደረቀውንም ፡ ጡት ፡ ስጣቸው ።

15 ፤ ክፋታቸው ፡ ኹሉ ፡ በገልገላ ፡ አለ ፤ በዚያ ፡ ጠልቻቸዋለኹ ፤ ስለሠሩት ፡ ክፋት ፡ ከቤቴ ፡ አሳድዳቸዋለኹ ፤ ከእንግዲህ ፡ ወዲያ ፡ አልወዳቸውም ፤ አለቃዎቻቸው ፡ ኹሉ ፡ ዐመፀኛዎች ፡ ናቸው ።

16 ፤ ኤፍሬም ፡ ተመታ ፥ ሥሩም ፡ ደረቀ ፥ ፍሬም ፡ አያፈራም ፤ ደግሞም ፡ ቢወልዱ ፡ የማሕፀናቸውን ፡ ፍሬ ፡ እገድላለኹ ።

17 ፤ አልሰሙትምና ፡ አምላኬ ፡ ይጥላቸዋል ፤ በአሕዛብም ፡ መካከል ፡ ተቅበዝባዦች ፡ ይኾናሉ ።

## ትንቢተ ፡ ሆሴዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 10 ።

ምዕራፍ ፡ 10 ።

1 ፤ እስራኤል ፡ ፍሬው ፡ የበዛለት ፡ የለመለመ ፡ ወይን ፡ ነው ፤ እንደ ፡ ፍሬው ፡ ብዛት ፡ መሠዊያውን ፡ አብዝቷል ፤ እንደ ፡ ምድሩም ፡ ማማር ፡ መጠን ፡ ሐውልቶችን ፡ እያሳመሩ ፡ ሠርተዋል ።

2 ፤ ልባቸው ፡ ተከፈለ ፤ አኹንም ፡ በደላቸውን ፡ ይሸከማሉ ፤ ርሱ ፡ መሠዊያቸውን ፡ ያፈርሳል ፥ ሐውልቶቻቸውን ፡ ያጠፋል ።

3 ፤ አኹንም ፦ ንጉሥ ፡ የለንም ፥ እግዚአብሔርን ፡ አልፈራንምና ፤ ንጉሥስ ፡ ምን ፡ ያደርግልናል ፧ ይላሉ ።

4 ፤ የማይረባውን ፡ ቃል ፡ ይናገራሉ ፤ ቃል ፡ ኪዳን ፡ በገቡ ፡ ጊዜ ፡ በሐሰት ፡ ይምላሉ ፤ ስለዚህ ፥ መርዛም ፡ ሣር ፡ በዕርሻ ፡ ትልም ፡ ላይ ፡ እንደሚበቅል ፥ መቅሠፍት ፡ ይበቅልባቸዋል ።

5 ፤ የሰማርያ ፡ ሰዎች ፡ ስለቤትአዌን ፡ እንቦሳ ፡ ይፈራሉ ፤ ክብሩም ፡ ከርሱ ፡ ዘንድ ፡ ወጥቷልና ፥ ሕዝቡ ፡ ያለቅሱለታል ፥ የጣዖቱ ፡ ካህናትም ፡ በሐዘን ፡ ይንተባተባሉ ።

6 ፤ ለንጉሡ ፡ ለኢያሪም ፡ እጅ ፡ መንሻ ፡ ይኾን ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ አሶር ፡ ይማረካል ፤ ኤፍሬምን ፡ ዕፍረት ፡ ይይዘዋል ፥ እስራኤልም ፡ በምክሩ ፡ ያፍራል ።

7 ፤ ሰማርያ ፡ ከንጉሧ ፡ ጋራ ፡ በውሃ ፡ ላይ ፡ እንዳለ ፡ ዐረፋ ፡ ጠፍታለች ።

8 ፤ የእስራኤል ፡ ኀጢአት ፡ የኾኑት ፡ የአዌን ፡ የኰረብታው ፡ መስገጃዎች ፡ ይፈርሳሉ ፤ ሾኽና ፡ አሜከላ ፡ በመሠዊያዎቻቸው ፡ ላይ ፡ ይበቅላል ፤ ተራራዎችንም ፦ ክደኑን ፥ ኰረብታዎችንም ፦ ውደቁብን ፡ ይሏቸዋል ።

9 ፤ እስራኤል ፡ ሆይ ፥ ከጊብዓ ፡ ዘመን ፡ ዠምረኽ ፡ ኀጢአትን ፡ ሠርተኻል ፤ በዚያ ፡ ጸንተዋል ፤ በጊብዓ ፡ ላይ ፡ ሰልፍ ፡ አይደርስባቸውምን ፧

10 ፤ በፈቀድኹም ፡ ጊዜ ፡ እገሥጻቸዋለኹ ፤ ስለ ፡ ኹለቱም ፡ ኀጢአታቸው ፡ በታሰሩ ፡ ጊዜ ፡ አሕዛብ ፡ ይሰበሰቡባቸዋል ።

11 ፤ ኤፍሬም ፡ ማበራየት ፡ እንደ ፡ ለመደች ፡ ጊደር ፡ ነው ፥ እኔ ፡ ግን ፡ በዐንገቱ ፡ ውብት ፡ እጫንበታለኹ ፤ በኤፍሬም ፡ ላይ ፡ እጠምድበታለኹ ፥ ይሁዳም ፡ ያርሳል ፥ ያዕቆብም ፡ ዐፈሩን ፡ ያለሰልሳል ።

12 ፤ እግዚአብሔር ፡ መጥቶ ፡ ጽድቅን ፡ እስኪያዘንብላችኹ ፡ ድረስ ፡ ርሱን ፡ የምትሹበት ፡ ዘመን ፡ ነውና ፥ ለእናንተ ፡ በጽድቅ ፡ ዝሩ ፥ እንደ ፡ ምሕረቱም ፡ መጠን ፡ ዕጨዱ ፥ ጥጋታችኹንም ፡ ዕረሱ ።

13 ፤ ክፋትን ፡ ዐርሳችኋል ፥ ኀጢአትንም ፡ ዐጭዳችኋል ፥ የሐሰትንም ፡ ፍሬ ፡ በልታችኋል ፤ በኀያላንኽ ፡ ብዛት ፥ በመንገድኽም ፡ ላይ ፡ ታምነኻልና ።

14 ፤ በሕዝብኽም ፡ መካከል ፡ ሽብር ፡ ይነሣል ፤ እናትም ፡ ከልጆቿ ፡ ጋራ ፡ በተፈጠፈጠች ፡ ጊዜ ፡ ሰልማን ፡ ቤትአርብኤልን ፡ በሰልፍ ፡ ቀን ፡ እንዳፈረሰ ፥ ዐምባዎችኽ ፡ ኹሉ ፡ ይፈርሳሉ ።

15 ፤ ከኀጢአታችኹም ፡ ክፋት ፡ የተነሣ ፡ ቤቴል ፡ እንዲሁ ፡ ያደርግባችኋል ፤ በነጋ ፡ ጊዜ ፡ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ፈጽሞ ፡ ይጠፋል ።

___________________ትንቢተ ፡ ሆሴዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 11 ። ___________________

ምዕራፍ ፡ 11 ።

1 ፤ እስራኤል ፡ ሕፃን ፡ በነበረ ፡ ጊዜ ፡ ወደድኹት ፥ ልጄንም ፡ ከግብጽ ፡ ጠራኹት ።

2 ፤ አብዝቼ ፡ ብጠራቸው ፡ አጥብቀው ፡ ከፊቴ ፡ ራቁ ፤ ለበዓሊምም ፡ ይሠዉ ፡ ነበር ፥ ለተቀረጹ ፡ ምስሎችም ፡ ያጥኑ ፡ ነበር ።

3 ፤ እኔም ፡ ኤፍሬምን ፡ ክንዱን ፡ ይዤ ፡ በእግሩ ፡ እንዲኼድ ፡ መራኹት ፤ እኔም ፡ እፈውሳቸው ፡ እንደ ፡ ነበር ፡ አላወቁም ።

4 ፤ በሰው ፡ ገመድ ፡ በፍቅርም ፡ እስራት ፡ ሳብኋቸው ፤ ለእነርሱም ፡ ቀምበርን ፡ ከጫንቃቸው ፡ ላይ ፡ እንደሚያነሣ ፡ ኾንኹ ፥ ድርቆሽም ፡ ጣልኹላቸው ።

5 ፤ ወደ ፡ እኔ ፡ ይመለሱ ፡ ዘንድ ፡ አልወደዱምና ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ ምድር ፡ ይመለሳሉ ፥ አሶርም ፡ ንጉሣቸው ፡ ይኾናል ።

6 ፤ ከመከሩትም ፡ ምክር ፡ የተነሣ ፡ ሰይፍ ፡ በከተማዎቻቸው ፡ ላይ ፡ ይወድቃል ፥ ከበርቴዎችንም ፡ ያጠፋል ።

7 ፤ ሕዝቤም ፡ ከእኔ ፡ ይመለሱ ፡ ዘንድ ፡ ወደዱ ፤ ወደ ፡ ላይም ፡ ቢጠሯቸው ፡ ማንም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደርጋቸው ፡ ዘንድ ፡ አይችልም ።

8 ፤ ኤፍሬም ፡ ሆይ ፥ እንዴት ፡ እጥልኻለኹ ፨ እስራኤል ፡ ሆይ ፥ እንዴትስ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጥኻለኹ ፨ እንዴትስ ፡ እንደ ፡ አዳማ ፡ እጥልኻለኹ ፨ እንዴትስ ፡ እንደ ፡ ሲባዮ ፡ አደርግኻለኹ ፨ ልቤ ፡ በውስጤ ፡ ተናውጣለች ፥ ምሕረቴም ፡ ተነሣሥታለች ።

9 ፤ እኔ ፡ አምላክ ፡ ነኝ ፡ እንጂ ፡ ሰው ፡ አይደለኹምና ፥ በመካከልኽም ፡ ቅዱሱ ፡ ነኝና ፡ የቍጣዬን ፡ መቅሠፍት ፡ አላደርግም ፥ ኤፍሬምንም ፡ አጠፋ ፡ ዘንድ ፡ አልመለስም ፤ በመዓትም ፡ አልመጣም ።

10 ፤ እግዚአብሔርን ፡ ይከተላሉ ፥ ርሱም ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ያገሣል ፤ ባገሣም ፡ ጊዜ ፡ ልጆች ፡ እየተንቀጠቀጡ ፡ ከምዕራብ ፡ ይመጣሉ ።

11 ፤ እንደ ፡ ወፍም ፡ ከግብጽ ፥ እንደ ፡ ርግብም ፡ ከአሶር ፡ ምድር ፡ እየተንቀጠቀጡ ፡ ይመጣሉ ፤ በቤታቸውም ፡ አኖራቸዋለኹ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

___________________ትንቢተ ፡ ሆሴዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 12 ። ___________________

ምዕራፍ ፡ 12 ።

1 ፤ ኤፍሬም ፡ በሐሰት ፥ የእስራኤልም ፡ ቤት ፡ በተንኰል ፡ ከበበኝ ፤ ይሁዳም ፡ ከታመነው ፡ ቅዱሱ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጋራ ፡ አይጸናም ።

2 ፤ ኤፍሬም ፡ ነፋስን ፡ ይበላል ፥ የምሥራቅንም ፡ ነፋስ ፡ ይከተላል ፤ ኹልጊዜም ፡ ሐሰትንና ፡ ተንኰልን ፡

ያበዛል ፤ ከአሶር ፡ ጋራ ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ያደርጋሉ ፥ ወደ ፡ ግብጽም ፡ ዘይት ፡ ይወስዳሉ ።

3 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ደግሞ ፡ ከይሁዳ ፡ ጋራ ፡ ክርክር ፡ አለው ፥ ያዕቆብንም ፡ እንደ ፡ መንገዱ ፡ ይቀጣል ፤ እንደ ፡
ሥራውም ፡ ይመልስለታል ።

4 ፤ በማሕፀን ፡ ውስጥ ፡ ወንድሙን ፡ በተረከዙ ፡ ያዘው ፥ በጕልማሳነቱም ፡ ጊዜ ፡ ከአምላክ ፡ ጋራ ፡ ታገለ ፤

5 ፤ ከመልአኩም ፡ ጋራ ፡ ታግሎ ፡ አሸነፈ ፤ አልቅሶም ፡ ለመነው ። በቤቴልም ፡ አገኘው ፥ በዚያም ፡ ከእኛ ፡ ጋራ ፡
ተነጋገረ ።

6 ፤ ርሱም ፡ የሰራዊት ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ፤ የመታሰቢያው ፡ ስም ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ።

7 ፤ ስለዚህ ፥ ወደ ፡ አምላክኽ ፡ ተመለስ ፤ ምሕረትንና ፡ ፍርድን ፡ ጠብቅ ፥ ዘወትርም ፡ በአምላክኽ ፡ ታመን ።

8 ፤ ከከነዓን ፡ ወገን ፡ ነው ፤ በእጁ ፡ የተንኰል ፡ ሚዛን ፡ አለ ፥ ሽንገላንም ፡ ይወዳል ።

9 ፤ ኤፍሬምም ፦ ባለጠጋ ፡ ኾኛለኹ ፥ ሀብትንም ፡ አግኝቻለኹ ፥ በድካሜም ፡ ኹሉ ፡ ኀጢአት ፡ የሚኾን ፡ በደል ፡
አይገኝብኝም ፡ አለ ።

10 ፤ እኔም ፡ ከግብጽ ፡ ዠምሬ ፡ አምላክኽ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ፤ እንደ ፡ ዓመት ፡ በዓል ፡ ቀን ፡ እንደ ፡ ገና ፡ በድንኳን ፡
እንድትኖር ፡ አደርግኻለኹ ።

11 ፤ ለነቢያትም ፡ ተናግሬያለኹ ፥ ራእይንም ፡ አብዝቻለኹ ፤ በነቢያትም ፡ እጅ ፡ ምሳሌዎችን ፡ አውጥቻለኹ ።

12 ፤ ኀጢአት ፡ በገለዓድ ፡ አለ ፤ ፈጽመው ፡ ከንቱ ፡ ናቸው ፤ ወይፈኖች ፡ በገልገላ ፡ ይሠዋሉ ፥ መሠዊያዎቻቸውም ፡
በዕርሻ ፡ ትልም ፡ ላይ ፡ የድንጋይ ፡ ክምር ፡ ይኾናሉ ።

13 ፤ ያዕቆብ ፡ ወደሶርያ ፡ አገር ፡ ሸሸ ፥ እስራኤልም ፡ ስለ ፡ ሚስት ፡ አገለገለ ፥ ስለ ፡ ሚስትም ፡ ጠባቂ ፡ ነበረ ።

14 ፤ እግዚአብሔርም ፡ በነቢይ ፡ እጅ ፡ እስራኤልን ፡ ከግብጽ ፡ አወጣ ፥ በነቢይም ፡ እጅ ፡ ጠበቀው ።

15 ፤ ኤፍሬም ፡ አስመርሮ ፡ አስቈጣው ፤ ስለዚህ ፥ ደሙ ፡ በላዩ ፡ ላይ ፡ ነው ፤ ጌታውም ፡ ስድቡን ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡
ይመልሳል ።

ትንቢተ ፡ ሆሴዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 13 ።

ምዕራፍ ፡ 13 ።

1 ፤ ኤፍሬም ፡ በተናገረ ፡ ጊዜ ፡ ፍርሀት ፡ ነበረ ፥ በእስራኤልም ፡ ዘንድ ፡ ታበየ ፤ ነገር ፡ ግን ፥ በዓልን ፡ በማምለክ ፡
በበደለ ፡ ጊዜ ፡ ሞተ ።

2 ፤ አኹንም ፡ ኀጢአትን ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ጨመሩ ፤ በብራቸውም ፡ ለራሳቸው ፡ ቀልጦ ፡ የተሠራ ፡ ምስልን ፥ እንደ ፡
ጥበባቸውም ፡ ጣዖታትን ፡ ሠርተዋል ፤ ኹሉም ፡ የሠራተኛ ፡ ሥራ ፡ ናቸው ። ስለ ፡ እነርሱም ፦ የሚሠዉ ፡ ሰዎች ፡
እንቦሳውን ፡ ይሳሙ ፡ ይላሉ ።

3 ፤ ስለዚህም ፡ እንደ ፡ ማለዳ ፡ ደመና ፥ በጧትም ፡ እንደሚያልፍ ፡ ጠል ፥ በዐውሎ ፡ ነፋስም ፡ ከዐውድማ ፡
እንደሚበተን ፡ እብቅ ፥ ከመስኮትም ፡ እንደሚወጣ ፡ ጢስ ፡ ይኾናሉ ።

4 ፤ እኔ ፡ ግን ፡ ከግብጽ ፡ ምድር ፡ ዠምሬ ፡ አምላክኽ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ፤ ከእኔም ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ አምላክ ፡
አታውቅም ፥ ከእኔም ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ መድኀኒት ፡ የለም ።

5 ፤ በምድረ ፡ በዳ ፥ እጅግ ፡ በደረቀ ፡ ምድር ፡ ዐውቄኽ ፡ ነበር ።

6 ፤ ከተሰማሩ ፡ በኋላ ፡ ጠገቡ ፥ በጠገቡም ፡ ጊዜ ፡ ልባቸው ፡ ታበየ ፤ ስለዚህ ፥ ረሱኝ ።

7 ፤ ስለዚህም ፡ እኔ ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ኾንኹባቸው ፥ እንደ ፡ ነብርም ፡ በመንገድ ፡ አጠገብ ፡ አደባባቸዋለኹ ፤

8 ፤ ልጇ ፡ እንደ ፡ ተነጠቀባት ፡ ድብ ፡ እገጥማቸዋለኹ ፥ የልባቸውንም ፡ ስብ ፡ እቀዳለኹ ፤ በዚያም ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡
እበላቸዋለኹ ፥ የምድረ ፡ በዳም ፡ አውሬ ፡ ይነጣጠቃቸዋል ።

9 ፤ እስራኤል ፡ ሆይ ፥ በእኔ ፡ በረዳትኽ ፡ ላይ ፡ በመነሣትኽ ፡ ጥፋትኽ ፡ ነው ።

10 ፤ በየከተማኽ ፡ ኹሉ ፡ ያድንኽ ፡ ዘንድ ፡ ንጉሥኽ ፡ ወዴት ፡ አለ ፧ ስለ ፡ እነርሱም ፦ ንጉሥንና ፡ አለቃዎችን ፡ ስጠኝ ፡ ብለኽ ፡ የተናገርኸው ፡ መሳፍንቶችኽ ፡ ወዴት ፡ አሉ ፧

11 ፤ በቍጣዬ ፡ ንጉሥን ፡ ሰጠኹኽ ፥ በመዓቴም ፡ ሻርኹት ።

12 ፤ የኤፍሬም ፡ በደል ፡ ታስሯል ፥ ኀጢአቱም ፡ ተከማችቷል ።

13 ፤ ምጥ ፡ እንደ ፡ ያዛት ፡ ሴት ፡ ጭንቅ ፡ ይመጣበታል ፤ በሚወለድበት ፡ ጊዜ ፡ በማሕፀን ፡ አፍ ፡ ቀጥ ፡ ብሎ ፡ አይወጣምና ፡ አእምሮ ፡ የሌለው ፡ ልጅ ፡ ነው ።

14 ፤ ከሲኦል ፡ እጅ ፡ እታደጋቸዋለኹ ፥ ከሞትም ፡ እቤዣቸዋለኹ ፤ ሞት ፡ ሆይ ፥ ቸነፈርኽ ፡ ወዴት ፡ አለ ፧ ሲኦል ፡ ሆይ ፥ ማጥፋትኽ ፡ ወዴት ፡ አለ ፧ ርኅራኄ ፡ ከዐይኔ ፡ ተሰወረች ።

15 ፤ በወንድሞቹ ፡ መካከል ፡ ፍሬያማ ፡ ቢኾን ፡ የምሥራቅ ፡ ነፋስ ፡ ይመጣል ፥ የእግዚአብሔር ፡ ነፋስ ፡ ከምድረ ፡ በዳ ፡ ይመጣል ፤ ምንጩንም ፡ ያደርቃል ፥ ፈሳሹንም ፡ ያጠፋል ፥ የተከበሩ ፡ ዕቃዎች ፡ ኹሉ ፡ ያሉበትን ፡ መዝገብ ፡ ይበዘብዛል ።

16 ፤ ሰማርያ ፡ በአምላኳ ፡ ላይ ፡ ዐምፃለችና ፡ በደሏን ፡ ትሸከማለች ፤ በሰይፍ ፡ ይወድቃሉ ፥ ሕፃኖቻቸውም ፡ ይፈጠፈጣሉ ፥ እርጕዞቻቸውም ፡ ይቀደዳሉ ።

ትንቢተ ፡ ሆሴዕ ፥ ምዕራፍ ፡ 14 ።

ምዕራፍ ፡ 14 ።

1 ፤ እስራኤል ፡ ሆይ ፥ በኀጢአትኽ ፡ ወድቀኻልና ፥ ወደ ፡ አምላክኽ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተመለስ ።

2 ፤ ከእናንተ ፡ ጋራ ፡ ቃልን ፡ ውሰዱ ፥ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ተመልሳችኹ ፦ ኀጢአትን ፡ ኹሉ ፡ አስወግድ ፥ በቸርነትም ፡ ተቀበለን ፥ በወይፈንም ፡ ፋንታ ፡ የከንፈራችንን ፡ ፍሬ ፡ እንሰጣለን ።

3 ፤ አሶር ፡ አያድነንም ፤ በፈረስ ፡ ላይ ፡ አንቀመጥም ፤ ድኻ ፡ አደጉም ፡ ባንተ ፡ ዘንድ ፡ ምሕረትን ፡ ያገኛልና ፥ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ለእጆቻችን ፡ ሥራ ። አምላኮቻችን ፡ ናችኹ ፡ አንላቸውም ፡ በሉት ።

4 ፤ ቍጣዬ ፡ ከርሱ ፡ ዘንድ ፡ ተመልሷልና ፥ ዐመፃቸውን ፡ እፈውሳለኹ ፥ በገዛ ፡ ፈቃዴ ፡ እወዳቸዋለኹ ።

5 ፤ ለእስራኤልም ፡ እንደ ፡ ጠል ፡ እኾነዋለኹ ፤ እንደ ፡ አበባም ፡ ያብባል ፥ እንደ ፡ ሊባኖስም ፡ ሥሩን ፡ ይሰዳል ።

6 ፤ ቅርንጫፎቹም ፡ ይዘረጋሉ ፥ ውበቱም ፡ እንደ ፡ ወይራ ፥ ሽታውም ፡ እንደ ፡ ሊባኖስ ፡ ይኾናል ።

7 ፤ ከጥላውም ፡ በታች ፡ የሚቀመጡ ፡ ይመለሳሉ ፤ ከእኽሉም ፡ የተነሣ ፡ ይጠግባሉ ፤ እንደ ፡ ወይንም ፡ ዐረግ ፡ ያብባሉ ፤ መታሰቢያውም ፡ እንደ ፡ ሊባኖስ ፡ ወይን ፡ ጠጅ ፡ ይኾናል ።

8 ፤ ከእንግዲህ ፡ ወዲያ ፡ ጣዖት ፡ ለኤፍሬም ፡ ምንድር ፡ ነው ፧ እኔ ፡ ሰምቼዋለኹ ፥ ወደ ፡ ርሱም ፡ እመለከታለኹ ፤ እኔ ፡ እንደ ፡ ለመለመ ፡ ጥድ ፡ ነኝ ፤ ፍሬኽ ፡ በእኔ ፡ ዘንድ ፡ ይገኛል ።

9 ፤ ይህን ፡ ነገር ፡ የሚያስተውል ፡ ጠቢብ ፥ የሚያውቃትም ፡ አስተዋይ ፡ ማን ፡ ነው ፧ የእግዚአብሔር ፡ መንገድ ፡ ቅን ፡ ነው ፥ ጻድቃንም ፡ ይኼዱበታል ፤ ተላላፊዎች ፡ ግን ፡ ይወድቁበታል ፨

# ትንቢተ ፡ ኢዮኤል ።

(ክለሳ.1.20020507)

_______________ትንቢተ ፡ ኢዮኤል ፥ ምዕራፍ ፡ 1 ። _______________

ምዕራፍ ፡ 1 ።

1 ፤ ወደባቱኤል ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ኢዮኤል ፡ የመጣው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ፦

2 ፤ እናንተ ፡ ሽማግሌዎች ፥ ይህን ፡ ስሙ ፤ በምድርም ፡ የምትኖሩ ፡ ኹሉ ፥ አድምጡ ። ይህ ፡ በዘመናችኹ ፡ ወይስ ፡ በአባቶቻችኹ ፡ ዘመን ፡ ኾኖ ፡ ነበርን ፧

3 ፤ ይህን ፡ ለልጆቻችኹ ፡ ንገሩ ፤ ልጆቻችኹም ፡ ለልጆቻቸው ፥ ልጆቻቸውም ፡ ለኋለኛው ፡ ትውልድ ፡ ይንገሩ ።

4 ፤ ከተምች ፡ የቀረውን ፡ አንበጣ ፡ በላው ፤ ከአንበጣም ፡ የቀረውን ፡ ደጎብያ ፡ በላው ፤ ከደጎብያም ፡ የቀረውን ፡ ኰብኰባ ፡ በላው ።

5 ፤ በተሓ ፡ ወይን ፡ ጠጃችኹ ፡ ከአፋችኹ ፡ ተወግዷልና ፥ እናንተ ፡ ሰካራሞች ፥ ነቅታችኹ ፡ አልቅሱ ፤ እናንተም ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ የምትጠጡ ፡ ኹሉ ፥ ዋይ ፡ በሉ ።

6 ፤ ቍጥርም ፡ የሌለው ፡ ብርቱ ፡ ሕዝብ ፡ በምድሬ ፡ ላይ ፡ ወጥቷልና ፤ ጥርሳቸው ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ጥርስ ፥ መንጋጋቸውም ፡ እንደ ፡ እንስቲቱ ፡ አንበሳ ፡ መንጋጋ ፡ ነው ።

7 ፤ ወይኔን ፡ ባዶ ፡ ምድር ፡ አደረገው ፥ በለሴንም ፡ ሰበረው ፤ ባዶም ፡ አደረገው ፥ ጣለውም ፤ ቅርንጫፎቹም ፡ ነጡ ።

8 ፤ ለቍንጅናዋ ፡ ባል ፡ ማቅ ፡ ለብሳ ፡ እንደምታለቅስ ፡ ድንግል ፡ አልቅሺ ።

9 ፤ የእኽሉ ፡ ቍርባንና ፡ የመጠጡ ፡ ቍርባን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ተወግዷል ፤ የእግዚአብሔርም ፡ አገልጋዮች ፡ ካህናቱ ፡ አለቀሱ ።

10 ፤ እኽሉ ፡ ጠፍቷልና ፥ ወይኑም ፡ ደርቋልና ፥ ዘይቱም ፡ ጎድሏልና ፥ ዕርሻው ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ኾኗል ፥ ምድሪቱም ፡ አልቅሳለች ።

11 ፤ መከሩ ፡ ከዕርሻቸው ፡ ጠፍቷልና ፥ ገበሬዎች ፡ ስለ ፡ ስንዴውና ፡ ስለ ፡ ገብሱ ፡ ዐፈሩ ፤ የወይን ፡ አትክልተኛዎችም ፡ አለቀሱ ።

12 ፤ ወይኑ ፡ ደርቋል ፥ በለሱም ፡ ጠውልጓል ፤ ሮማኑና ፡ ተምሩ ፡ እንኰዩም ፡ የምድርም ፡ ዛፎች ፡ ኹሉ ፡ ደርቀዋል ፤ ደስታም ፡ ከሰው ፡ ልጆች ፡ ዘንድ ፡ ርቋል ።

13 ፤ የእኽሉ ፡ ቍርባንና ፡ የመጠጡ ፡ ቍርባን ፡ ከአምላካችኹ ፡ ቤት ፡ ቀርቷልና ፥ እናንተ ፡ ካህናት ፥ ማቅ ፡ ታጥቃችኹ ፡ አልቅሱ ፤ እናንተም ፡ የመሠዊያ ፡ አገልጋዮች ፥ ዋይ ፡ በሉ ፤ እናንተ ፡ የአምላኬ ፡ አገልጋዮች ፥ ኑ ፥ ሌሊቱን ፡ ኹሉ ፡ በማቅ ፡ ላይ ፡ ተኙ ።

14 ፤ ጾምን ፡ ቀድሱ ፥ ጉባኤውንም ፡ ዐውጁ ፤ ሽማግሌዎችንና ፡ በምድር ፡ የሚኖሩትን ፡ ኹሉ ፡ ወደ ፡ አምላካችኹ ፡ ወደእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ሰብስቡ ፥ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ጩኹ ።

15 ፤ የእግዚአብሔር ፡ ቀን ፡ ቀርቧልና ፥ ለቀኑ ፡ ወዮ! ርሱም ፡ ኹሉን ፡ ከሚችል ፡ ከአምላክ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ጥፋት ፡ ይመጣል ።

16 ፤ ከዐይናችን ፡ ፊት ፡ ምግብ ፥ ከአምላካችንም ፡ ቤት ፡ ደስታና ፡ እልልታ ፡ የጠፉ ፡ አይደለምን ፧

17 ፤ ዘሩ ፡ በምድር ፡ ውስጥ ፡ በሰበሰ ፤ እኽሉ ፡ ደርቋልና ፥ ጎተራዎቹ ፡ ባዶ ፡ ናቸው ፥ ጎታዎቹም ፡ ፈርሰዋል ።

18 ፤ እንስሳዎች ፡ እጅግ ፡ ጮኹ ፤ የላምም ፡ መንጋዎች ፡ ማሰማሪያ ፡ የላቸውምና ፡ ተጠራጠሩ ፤ የበግም ፡ መንጋዎች ፡

ጠፍተዋል ።

19 ፤ አቤቱ ፥ እሳት ፡ የምድረ ፡ በዳውን ፡ ማሰማሪያ ፡ በልቷልና ፥ ነበልባሉም ፡ የዱሩን ፡ ዛፍ ፡ ሹሉ ፡
አቃጥሏልና ፥ ወዳንተ ፡ እጮኻለኹ ።

20 ፤ ፈሳሹ ፡ ውሃ ፡ ደርቋልና ፥ እሳቱም ፡ የምድረ ፡ በዳውን ፡ ማሰማሪያ ፡ በልቷልና ፥ የምድር ፡ አራዊት ፡ ወዳንተ ፡
አለከለኩ ።

ትንቢተ ፡ ኢዮኤል ፥ ምዕራፍ ፡ 2 ።

ምዕራፍ ፡ 2 ።

1 ፤ የእግዚአብሔር ፡ ቀን ፡ መጥቷልና ፥ ርሱም ፡ ቀርቧልና ፥ በጽዮን ፡ መለከትን ፡ ንፉ ፥ በቅዱሱም ፡ ተራራዬ ፡ ላይ ፡
እሪ ፡ በሉ ፤ በምድርም ፡ የሚኖሩ ፡ ሹሉ ፡ ይንቀጥቀጡ ፤ የእግዚአብሔር ፡ ቀን ፡ መጥቷልና ፤

2 ፤ የጨለማና ፡ የጭጋግ ፡ ቀን ፥ የደመናና ፡ የድቅድቅ ፡ ጨለማ ፡ ቀን ፡ ነው ፤ ታላቅና ፡ ብርቱ ፡ ሕዝብ ፡ በተራራዎች ፡
ላይ ፡ እንደ ፡ ወገግታ ፡ ተዘርግቷል ፤ ከዘለዓለምም ፡ ዠምሮ ፡ እንደ ፡ እነርሱ ፡ ያለ ፡ አልነበረም ፥ ከነርሱም ፡ በዃላ ፡
እስከ ፡ ብዙ ፡ ትውልድ ፡ ድረስ ፡ እንደ ፡ እነርሱ ፡ ያለ ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አይኾንም ።

3 ፤ እሳት ፡ በፊታቸው ፡ ትባላለች ፥ በዃላቸውም ፡ ነበልባል ፡ ታቃጥላለች ፤ ምድሪቱ ፡ በፊታቸው ፡ እንደ ፡ ዔዶን ፡
ገነት ፥ በዃላቸውም ፡ የምድረ ፡ በዳ ፡ በረሓ ፡ ናት ፤ ከነርሱም ፡ የሚያመልጥ ፡ የለም ።

4 ፤ መልካቸው ፡ እንደ ፡ ፈረስ ፡ መልክ ፡ ነው ፥ እንደ ፡ ፈረሰኞችም ፡ ይሮጣሉ ።

5 ፤ በተራራ ፡ ላይ ፡ እንዳሉ ፡ ሠረገላዎች ፡ ድምፅ ፥ ገለባውንም ፡ እንደሚበላ ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ ነበልባል ፡
ድምፅ ፥ ለሰልፍም ፡ እንደ ፡ ተዘጋጀ ፡ እንደ ፡ ብርቱ ፡ ሕዝብ ፡ ያኰበኵባሉ ።

6 ፤ ከፊታቸው ፡ አሕዛብ ፡ ይንቀጠቀጣሉ ፤ የሰውም ፡ ፊት ፡ ሹሉ ፡ ይጠቍራል ።

7 ፤ እንደ ፡ ኀያላን ፡ ይሮጣሉ ፥ እንደ ፡ ሰልፈኛዎችም ፡ በቅጥሩ ፡ ላይ ፡ ይወጣሉ ፤ እያንዳንዱም ፡ በመንገዱ ፡ ላይ ፡
ይራመዳል ፥ ከርምጃቸውም ፡ አያፈገፍጉም ።

8 ፤ አንዱ ፡ ካንዱ ፡ ጋራ ፡ አይጋፋም ፥ እያንዳንዱም ፡ መንገዱን ፡ ይጠበጥባል ፤ በሰልፍ ፡ መካከል ፡
ያልፋሉ ፥ እነርሱም ፡ አይቈስሉም ።

9 ፤ በከተማም ፡ ያኰበኵባሉ ፥ በቅጥሩም ፡ ላይ ፡ ይሮጣሉ ፤ ወደ ፡ ቤቶችም ፡ ይወጣሉ ፥ እንደ ፡ ሌባም ፡ በመስኮቶች ፡
ይገባሉ ።

10 ፤ ምድሪቱም ፡ ከፊታቸው ፡ ትናወጣለች ፥ ሰማያትም ፡ ይንቀጠቀጣሉ ፤ ፀሓይና ፡ ጨረቃም ፡
ይጨልማሉ ፥ ከዋክብትም ፡ ብርሃናቸውን ፡ ይሰውራሉ ።

11 ፤ እግዚአብሔርም ፡ በሰራዊቱ ፡ ፊት ፡ ድምፁን ፡ ይሰጣል ፤ ሰፈሩ ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ነውና ፥ ቃሉንም ፡ የሚያደርግ ፡
ርሱ ፡ ኀያል ፡ ነውና ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቀን ፡ ታላቅና ፡ እጅግ ፡ የሚያስፈራ ፡ ነውና ፥ ማን ፡ ይችለዋል ፧

12 ፤ አኹንስ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፥ በፍጹም ፡ ልባችኹ ፥ በጾምም ፥ በልቅሶና ፡ በዋይታ ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ ተመለሱ ።

13 ፤ ልባችኹን ፡ እንጂ ፡ ልብሳችኹን ፡ አትቅደዱ ፤ አምላካችኹም ፡ እግዚአብሔር ፡ ቸርና ፡ መሓሪ ፥ ቍጣው ፡
የዘገየ ፥ ምሕረቱም ፡ የበዛ ፥ ለክፋትም ፡ የተጸጸተ ፡ ነውና ፥ ወደ ፡ ርሱ ፡ ተመለሱ ።

14 ፤ የሚመለስና ፡ የሚጸጸት ፡ እንደ ፡ ኾነ ፥ ለአምላካችኹም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የእኽልና ፡ የመጠጥ ፡ ቍርባን ፡
የሚኾነውን ፡ በረከት ፡ የሚያተርፍ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ ማን ፡ ያውቃል ፧

15 ፤ በጽዮን ፡ መለከትን ፡ ንፉ ፥ ጾምንም ፡ ቀድሱ ፥ ጉባኤውንም ፡ ዐውጁ ፥

16 ፤ ሕዝቡንም ፡ አከማቹ ፥ ማኅበሩንም ፡ ቀድሱ ፥ ሽማግሌዎቹንም ፡ ሰብስቡ ፥ ሕፃናቱንና ፡ ጡት ፡ የሚጠቡትን ፡
አከማቹ ፤ ሙሽራው ፡ ከዕልፍኙ ፥ ሙሽራዪቱም ፡ ከጫጕላዋ ፡ ይውጡ ።

17 ፤ የእግዚአብሔርም ፡ አገልጋዮች ፡ ካህናት ፡ ከወለሉና ፡ ከመሠዊያው ፡ መካከል ፡ እያለቀሱ ፦ አቤቱ ፥ ለሕዝብኽ ፡

ራራ ፤ አሕዛብም ፡ እንዳይነቀፏቸው ፡ ርስትኽን ፡ ለማላገጫ ፡ አሳልፈኽ ፡ አትስጥ ፤ ከአሕዛብ ፡ መካከል ፦ አምላካቸው ፡ ወዴት ፡ ነው ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ይላሉ ፡ ይበሉ ።

18 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ስለ ፡ ምድሩ ፡ ቀና ፤ ለሕዝቡም ፡ ራራለት ።

19 ፤ እግዚአብሔርም ፡ መልሶ ፡ ሕዝቡን ፦ እንሆ ፤ እኽልንና ፡ ወይንን ፡ ዘይትንም ፡ እሰድላችኋለኹ ፤ እናንተም ፡ በርሱ ፡ ትጠግባላችኹ ፤ ከእንግዲህም ፡ ወዲያ ፡ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ መሰደቢያ ፡ አላደርጋችኹም ።

20 ፤ የሰሜንንም ፡ ሰራዊት ፡ ከእናንተ ፡ ዘንድ ፡ አርቃለኹ ፤ ወደ ፡ በረሓና ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፤ ፊቱን ፡ ወደምሥራቁ ፡ ባሕር ፡ ኋርባውንም ፡ ወደምዕራቡ ፡ ባሕር ፡ አድርጌ ፡ አሳድደዋለኹ ፤ ርሱም ፡ ትዕቢትን ፡ አድርጓልና ፤ ግማቱ ፡ ይወጣል ፤ ክርፋቱም ፡ ይነሣል ፡ አለ ።

21 ፤ ምድር ፡ ሆይ ፤ እግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፡ ነገር ፡ አድርጓልና ፤ አትፍሪ ፤ ደስም ፡ ይበልሽ ፤ እልልም ፡ በዪ ።

22 ፤ እናንተ ፡ የምድር ፡ እንስሳዎች ፡ ሆይ ፤ የምድረ ፡ በዳው ፡ ማሰማሪያ ፡ ለምልሟልና ፤ ዛፉም ፡ ፍሬውን ፡ አፍርቷልና ፤ በለሱና ፡ ወይኑም ፡ ኀይላቸውን ፡ ሰጥተዋልና ፤ አትፍሩ ።

23 ፤ እናንተ ፡ የጽዮን ፡ ልጆች ፤ አምላካችኹ ፡ እግዚአብሔር ፡ የፊተኛውን ፡ ዝናብ ፡ በጽድቅ ፡ ሰጥቷችኋልና ፤ እንደ ፡ ቀድሞውም ፡ የፊተኛውንና ፡ የኋለኛውን ፡ ዝናብ ፡ አዝንቦላችኋልና ፤ በርሱ ፡ ደስ ፡ ይበላችኹ ፤ ለርሱም ፡ እልል ፡ በሉ ።

24 ፤ ዐውድማዎችም ፡ እኽልን ፡ ይሞላሉ ፤ መጥመቂያዎችም ፡ የወይን ፡ ጠጅንና ፡ ዘይትን ፡ አትረፍርፈው ፡ ያፈሳሉ ።

25 ፤ የሰደድኹባችኹ ፡ ታላቁ ፡ ሰራዊቴ ፡ አንበጣና ፡ ደጎብያ ፡ ኵብኵባና ፡ ተምች ፡ የበላቸውን ፡ ዓመታት ፡ እመልስላችኋለኹ ።

26 ፤ ብዙ ፡ መብል ፡ ትበላላችኹ ፤ ትጠግቡማላችኹ ፤ ከእናንተም ፡ ጋራ ፡ ተኣምራትን ፡ የሠራውን ፡ የአምላካችኹን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ ታመሰግናላችኹ ፤ ሕዝቤም ፡ ለዘለዓለም ፡ አያፍርም ።

27 ፤ እኔም ፡ በእስራኤል ፡ መካከል ፡ እንዳለኹ ፤ እኔም ፡ አምላካችኹ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ኾንኹ ፤ ከእኔም ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ አምላክ ፡ እንደሌለ ፡ ታውቃላችኹ ፤ ሕዝቤም ፡ ለዘለዓለም ፡ አያፍርም ።

28 ፤ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ እንዲህ ፡ ይኾናል ፤ መንፈሴን ፡ በሥጋ ፡ ለባሽ ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፡ አፈሳለኹ ፤ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻችኹም ፡ ትንቢት ፡ ይናገራሉ ፤ ሽማግሌዎቻችኹም ፡ ሕልምን ፡ ያልማሉ ፤ ጐበዞቻችኹም ፡ ራእይ ፡ ያያሉ ፤

29 ፤ ደግሞም ፡ በዚያ ፡ ወራት ፡ በወንዶችና ፡ በሴቶች ፡ ባሪያዎች ፡ ላይ ፡ መንፈሴን ፡ አፈሳለኹ ፤

30 ፤ በላይ ፡ በሰማይ ፡ ድንቆችን ፡ አሳያለኹ ፤ በታች ፡ በምድርም ፡ ደምና ፤ እሳት ፤ የጢስም ፡ ጭጋግ ።

31 ፤ ታላቁና ፡ የሚያስፈራው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቀን ፡ ሳይመጣ ፡ ፀሓይ ፡ ወደ ፡ ጨለማ ፤ ጨረቃም ፡ ወደ ፡ ደም ፡ ይለወጣል ።

32 ፤ እንዲህም ፡ ይኾናል ፤ የእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ የሚጠራ ፡ ኹሉ ፡ ይድናል ፤ እግዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፤ በጽዮን ፡ ተራራና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ መድኀኒት ፡ ይገኛል ። ደግሞም ፡ እግዚአብሔር ፡ የጠራቸው ፤ የምሥራች ፡ የሚሰበከላቸው ፡ ይገኛሉ ።

## ትንቢተ ፡ ኢዩኤል ፤ ምዕራፍ ፡ 3 ።

ምዕራፍ ፡ 3 ።

1 ፤ እንሆም ፤ በዚያ ፡ ወራትና ፡ በዚያ ፡ ዘመን ፤ የይሁዳንና ፡ የኢየሩሳሌምን ፡ ምርኮ ፡ በምመልስበት ፡ ጊዜ ፤

2 ፤ አሕዛብን ፡ ኹሉ ፡ ሰብስቤ ፡ ወደኢዮሳፍጥ ፡ ሸለቆ ፡ አወርዳቸዋለኹ ፤ በዚያም ፡ ስለ ፡ ሕዝቤና ፡ ስለ ፡ ርስቴ ፡ ስለ ፡ እስራኤል ፡ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ የበተኗቸውን ፡ ምድሬንም ፡ የተካፈሏትን ፡ እፋረድባቸዋለኹ ።

3 ፤ በሕዝቤም ፡ ላይ ፡ ዕጣ ፡ ተጣጣሉ ፤ ወንድ ፡ ልጅን ፡ ለጋለሞታ ፡ ዋጋ ፡ ሰጡ ፤ ሴት ፡ ልጅን ፡ ለወይን ፡ ጠጅ ፡ ሸጡ ፤ ጠጡም ።

4 ፤ ጢሮስና ፡ ሲዶና ፡ የፍልስጥኤምም ፡ ግዛት ፡ ኹሉ ፡ ሆይ ፤ ከእናንተ ፡ ጋራ ፡ ለእኔ ፡ ምን ፡ አለኝ ፡ በእውኑ ፡

ብድራትን ፡ ትመልሱልኛላችኹን ፥ ብድራትን ፡ ብትመልሱልኝ ፡ ፈጥኜ ፡ በችኰላ ፡ ብድራታችኹን ፡ በራሳችኹ ፡ ላይ ፡
እመልሳለኹ ።

5 ፤ ብሬንና ፡ ወርቄን ፡ ወስዳችኋልና ፥ የተወደደውንም ፡ መልካሙን ፡ ዕቃዬን ፡ ወደ ፡ መቅደሳችኹ ፡
አግብታችኋልና ፥

6 ፤ ከዳርቻቸውም ፡ ታርቋቸው ፡ ዘንድ ፡ የይሁዳንና ፡ የኢየሩሳሌምን ፡ ልጆች ፡ ለግሪክ ፡ ሰዎች ፡ ሸጣችኋልና ፥

7 ፤ እንሆ ፥ እነርሱን ፡ ከሸጣችኹበት ፡ ስፍራ ፡ አስነሣቸዋለኹ ፥ ብድራታችኹንም ፡ በራሳችኹ ፡ ላይ ፡ እመልሳለኹ ።

8 ፤ እግዚአብሔር ፡ ተናግሯልና ፥ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻችኹን ፡ በይሁዳ ፡ ልጆች ፡ እጅ ፡ እሸጣለኹ ፥ እነርሱም ፡
ለሩቆቹ ፡ ሕዝብ ፡ ለሳባ ፡ ሰዎች ፡ ይሸጧችኋል ።

9 ፤ ይህን ፡ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ ዐውጁ ፡ ለሰልፍ ፡ ተዘጋጁ ፡ ኀያላንን ፡ አስነሡ ፡ ሰልፈኞች ፡ ዅሉ ፡ ይቅረቡ ፡
ይውጡም ።

10 ፤ ማረሻችኹን ፡ ሰይፍ ፥ ማጭዳችኹንም ፡ ጦር ፡ ለማድረግ ፡ ቀጥቅጡ ፤ ደካማውም ፦ እኔ ፡ ብርቱ ፡ ነኝ ፡ ይበል ።

11 ፤ እናንተ ፡ በዙሪያ ፡ ያላችኹ ፡ አሕዛብ ፡ ዅሉ ፥ ቸኵላችኹ ፡ ኑ ፥ ተሰብሰቡ ፤ አቤቱ ፥ ኀያላንኽን ፡ ወደዚያ ፡
አውርድ ።

12 ፤ አሕዛብ ፡ ይነሡ ፥ ወደኢዮሳፍጥ ፡ ሸለቆም ፡ ይውጡ ፤ በዙሪያ ፡ ባሉ ፡ አሕዛብ ፡ ዅሉ ፡ ላይ ፡ እፈርድ ፡ ዘንድ ፡
በዚያ ፡ እቀመጣለኹና ።

13 ፤ መከሩ ፡ ደርሷልና ፥ ማጭድ ፡ ስደዱ ፤ መጥመቂያውም ፡ ሞልቷልና ፥ ኑ ፡ ርገጡ ፤ ከፋታቸውም ፡
በዝቷልና ፥ መጥመቂያ ፡ ዅሉ ፡ ፈርሷል ።

14 ፤ የእግዚአብሔር ፡ ቀን ፡ በፍርድ ፡ ሸለቆ ፡ ቀርቧልና ፥ የብዙ ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ውካታ ፡ በፍርድ ፡ ሸለቆ ፡ አለ ።

15 ፤ ፀሓይና ፡ ጨረቃ ፡ ጨልመዋል ፥ ከዋክብትም ፡ ብርሃናቸውን ፡ ሰውረዋል ።

16 ፤ እግዚአብሔርም ፡ በጽዮን ፡ ኾኖ ፡ ድምፁን ፡ ከፍ ፡ አድርጎ ፡ ይጮኻል ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ ኾኖ ፡ ቃሉን ፡
ይሰጣል ፤ ሰማይና ፡ ምድርም ፡ ይናወጣሉ ፤ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ለሕዝቡ ፡ መሸሸጊያ ፥ ለእስራኤልም ፡ ልጆች ፡
መጠጊያ ፡ ይኾናል ።

17 ፤ እኔም ፡ በተቀደሰው ፡ ተራራዬ ፡ በጽዮን ፡ የምቀመጥ ፡ አምላካችኹ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ኾንኹ ፡
ታውቃላችኹ ፤ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ኢየሩሳሌም ፡ የተቀደሰች ፡ ትኾናለች ፥ እንግዳዎችም ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡
አያልፉባትም ።

18 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ እንዲህ ፡ ይኾናል ፤ ተራራዎች ፡ በተሓ ፡ ጠጅ ፡ ያንጠባጥባሉ ፥ ኰረብታዎችም ፡ ወተትን ፡
ያፈሳሉ ፥ በይሁዳም ፡ ያሉት ፡ ፈፋዎች ፡ ዅሉ ፡ ውሃን ፡ ያጐርፋሉ ፡ ከእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ ምንጭ ፡
ትፈልቃለች ፥ የሰጢምንም ፡ ሸለቆ ፡ ታጠጣለች ።

19 ፤ በአገራቸው ፡ ንጹሑን ፡ ደም ፡ አፍሰዋልና ፥ በይሁዳ ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ ስላደረጉት ፡ ግፍ ፡ ግብጽ ፡ ምድረ ፡
በዳ ፥ ኤዶምያስም ፡ በረሓ ፡ ይኾናል ።

20 ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ይሁዳ ፡ ለዘለዓለም ፥ ኢየሩሳሌምም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ መኖሪያ ፡ ይኾናል ።

21 ፤ እኔም ፡ ንጹሕ ፡ ያላደረግኹትን ፡ ደማቸውን ፡ ንጹሕ ፡ አደርገዋለኹ ፥ እግዚአብሔርም ፡ በጽዮን ፡ ያድራል ፨

# ትንቢተ ፡ ዓሞጽ ።

(ክለሳ.1.20020507)

______________ትንቢተ ፡ ዓሞጽ ፥ ምዕራፍ ፡ 1 ። ______________

ምዕራፍ ፡ 1 ።

1 ፤ በቴቁሔ ፡ ከላም ፡ ጠባቂዎች ፡ መካከል ፡ የነበረ ፡ ዓሞጽ ፡ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በዖዝያን ፡ ዘመን ፥ በእስራኤልም ፡ ንጉሥ ፡ በዮአስ ፡ ልጅ ፡ በኢዮርብዓም ፡ ዘመን ፥ የምድር ፡ መናወጥ ፡ ከኾነበቱ ፡ ከኹለት ፡ ዓመት ፡ በፊት ፡ ስለ ፡ እስራኤል ፡ ያየው ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ፦

2 ፤ እንዲህም ፡ አለ ፦ እግዚአብሔር ፡ በጽዮን ፡ ኾኖ ፡ ድምፁን ፡ ከፍ ፡ አድርጎ ፡ ይጮኻል ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ ኾኖ ፡ ቃሉን ፡ ይሰጣል ፤ የእረኛዎችም ፡ ማሰማሪያዎች ፡ ያለቅሳሉ ፥ የቀርሜሎስም ፡ ራስ ፡ ይደርቃል ።

3 ፤ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ገለዓድን ፡ በብረት ፡ መንኰራኵር ፡ አኺዷልና ፥ ስለ ፡ ሦስት ፡ ወይም ፡ ስለ ፡ አራት ፡ የደማስቆ ፡ ኀጢአት ፡ መቅሠፍቴን ፡ ከማድረግ ፡ አልመለስም ።

4 ፤ በአዛሄል ፡ ቤት ፡ እሳትን ፡ እሰዳለኹ ፥ የወልደ ፡ አዴርንም ፡ አዳራሾች ፡ ትበላለች ።

5 ፤ የደማስቆንም ፡ መወርወሪያ ፡ እሰብራለኹ ፥ ተቀማጮችንም ፡ ከአዌን ፡ ሸለቆ ፡ አጠፋለኹ ፥ በትር ፡ የያዘውንም ፡ ከዔዴን ፡ ቤት ፡ አጠፋለኹ ፤ የሶርያም ፡ ሕዝብ ፡ ወደ ፡ ቂር ፡ ይማረካል ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

6 ፤ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ለኤዶምያስ ፡ አሳልፈው ፡ ይሰጧቸው ፡ ዘንድ ፡ ምርኮኛዎችን ፡ ኹሉ ፡ ማርከዋልና ፥ ስለ ፡ ሦስት ፡ ወይም ፡ ስለ ፡ አራት ፡ የጋዛ ፡ ኀጢአት ፡ መቅሠፍቴን ፡ ከማድረግ ፡ አልመለስም ።

7 ፤ በጋዛ ፡ ቅጥር ፡ ላይ ፡ እሳትን ፡ እሰዳለኹ ፥ አዳራሾቿንም ፡ ትበላለች ።

8 ፤ ተቀማጮችን ፡ ከአዛጦን ፡ አጠፋለኹ ፥ በትር ፡ የያዘውንም ፡ ከአስቀሎና ፡ አጠፋለኹ ፤ እጄንም ፡ በዐቃሮን ፡ ላይ ፡ እመልሳለኹ ፥ ከፍልስጥኤማውያንም ፡ የቀሩት ፡ ይጠፋሉ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

9 ፤ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ምርኮኛዎችን ፡ ኹሉ ፡ ለኤዶምያስ ፡ አሳልፈው ፡ ሰጥተዋልና ፥ የወንድሞችንም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አላሰቡምና ፡ ስለ ፡ ሦስት ፡ ወይም ፡ ስለ ፡ አራት ፡ የጢሮስ ፡ ኀጢአት ፡ መቅሠፍቴን ፡ ከማድረግ ፡ አልመለስም ።

10 ፤ በጢሮስ ፡ ቅጥር ፡ ላይ ፡ እሳትን ፡ እሰዳለኹ ፥ አዳራሾቿንም ፡ ትበላለች ።

11 ፤ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ወንድሙን ፡ በሰይፍ ፡ አሳዶታልና ፥ ርኅራኄንም ፡ ኹሉ ፡ ጥሏልና ፥ ቍጣውም ፡ ኹልጊዜ ፡ ቀዷልና ፥ መዓቱንም ፡ ለዘለዓለም ፡ ጠብቋልና ፥ ስለ ፡ ሦስት ፡ ወይም ፡ ስለ ፡ አራት ፡ የኤዶምያስ ፡ ኀጢአት ፡ መቅሠፍቴን ፡ ከማድረግ ፡ አልመለስም ።

12 ፤ በቴማን ፡ ላይ ፡ እሳትን ፡ እሰዳለኹ ፥ የባሶራንም ፡ አዳራሾች ፡ ትበላለች ።

13 ፤ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ዳርቻቸውን ፡ ያሰፉ ፡ ዘንድ ፡ የገለዓድን ፡ እርጉዞች ፡ ቀደዋልና ፥ ስለ ፡ ሦስት ፡ ወይም ፡ ስለ ፡ አራት ፡ የዐሞን ፡ ልጆች ፡ ኀጢአት ፡ መቅሠፍቴን ፡ ከማድረግ ፡ አልመለስም ።

14 ፤ በረባት ፡ ቅጥር ፡ ላይ ፡ እሳትን ፡ አነዳለኹ ፤ በሰልፍም ፡ ቀን ፡ በጩኸት ፡ በዐውሎ ፡ ነፋስም ፡ ቀን ፡ በሁከት ፡ አዳራሾቿን ፡ ትበላለች ፤

15 ፤ ንጉሣቸውም ፡ ከአለቃዎቹ ፡ ጋራ ፡ በአንድነት ፡ ይማረካል ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

______________ትንቢተ ፡ ዓሞጽ ፥ ምዕራፍ ፡ 2 ። ______________

ምዕራፍ ፡ 2 ።

1 ፤ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ የኤዶምያስን ፡ ንጉሥ ፡ ዐጥንት ፡ ዐመድ ፡ እስኪኾን ፡ ድረስ ፡

አቃጥሎታልና ፥ ስለ ፡ ሦስት ፡ ወይም ፡ ስለ ፡ አራት ፡ የሞዐብ ፡ ኀጢአት ፡ መቅሠፍቴን ፡ ከማድረግ ፡ አልመለስም ።

2 ፤ በሞዐብ ፡ ላይ ፡ እሳትን ፡ እሰዳለኹ ፥ የቂርዮትንም ፡ አዳራሾች ፡ ትበላለች ፤ ሞዐብም ፡ በውካታና ፡ በጩኸት ፡ በመለከትም ፡ ድምፅ ፡ ይሞታል ፤

3 ፤ ፈራጅንም ፡ ከመካከሏ ፡ አጠፋለኹ ፥ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ አለቃዎቿን ፡ ኹሉ ፡ እገድላለኹ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

4 ፤ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ ጥለዋልና ፥ ትእዛዙንም ፡ አልጠበቁምና ፥ አባቶቻቸውም ፡ የተከተሉት ፡ ሐሰታቸው ፡ አስቷቸዋልና ፥ ስለ ፡ ሦስት ፡ ወይም ፡ ስለ ፡ አራት ፡ የይሁዳ ፡ ኀጢአት ፡ መቅሠፍቴን ፡ ከማድረግ ፡ አልመለስም ።

5 ፤ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ እሳትን ፡ እሰዳለኹ ፥ የኢየሩሳሌምንም ፡ አዳራሾች ፡ ትበላለች ።

6 ፤ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ጻድቁን ፡ ስለ ፡ ብር ፥ ችጋረኛውንም ፡ ስለ ፡ አንድ ፡ ጥንድ ፡ ጫማ ፡ ሸጠውታልና ፥ ስለ ፡ ሦስት ፡ ወይም ፡ ስለ ፡ አራት ፡ የእስራኤል ፡ ኀጢአት ፡ መቅሠፍቴን ፡ ከማድረግ ፡ አልመለስም ።

7 ፤ የድኻዎችን ፡ ራስ ፡ በምድር ፡ ትቢያ ፡ ላይ ፡ ይረግጣሉ ፥ የትሑታንንም ፡ መንገድ ፡ ያጣምማሉ ፤ ቅዱሱንም ፡ ስሜን ፡ ያረክሱ ፡ ዘንድ ፡ አባትና ፡ ልጁ ፡ ወደ ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ ይገባሉ ፤

8 ፤ በመሠዊያውም ፡ ኹሉ ፡ አጠገብ ፡ ለመያዣነት ፡ በተወሰደው ፡ ልብስ ፡ ላይ ፡ ይተኛሉ ፤ በአምላካቸውም ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ በካሣ ፡ የተወሰደውን ፡ ወይን ፡ ጠጅ ፡ ይጠጣሉ ።

9 ፤ እኔ ፡ ግን ፡ ቁመቱ ፡ እንደ ፡ ዝግባ ፡ ቁመት ፥ ብርታቱም ፡ እንደ ፡ ኮምበል ፡ ዛፍ ፡ የነበረውን ፡ አሞራዊውን ፡ ከፊታቸው ፡ አጠፋኹ ፤ ፍሬውንም ፡ ከላዩ ፥ ሥሩንም ፡ ከታቹ ፡ አጠፋኹ ።

10 ፤ የአሞራዊውንም ፡ ምድር ፡ ትወርሱ ፡ ዘንድ ፡ ከግብጽ ፡ ምድር ፡ አወጣኋችኹ ፥ በምድረ ፡ በዳም ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡ መራኋችኹ ።

11 ፤ ከወንድ ፡ ልጆቻችኹም ፡ ነቢያትን ፥ ከጕበዛዝታችኹም ፡ ናዝራውያንን ፡ አስነሣኹ ፤ እናንተ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፥ ይህ ፡ እንደዚህ ፡ አይደለምን ፧ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

12 ፤ እናንተ ፡ ግን ፡ ናዝራውያኑን ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ አጠጣችኋቸው ፤ ነቢያቱንም ፦ ትንቢትን ፡ አትናገሩ ፡ ብላችኹ ፡ አዘዛችኋቸው ።

13 ፤ እንሆ ፥ ነዶ ፡ የተሞላች ፡ ሠረገላ ፡ እንደምትደቀድቅ ፡ እንዲሁ ፡ እደቀድቃችኋለኹ ።

14 ፤ ከሯጪም ፡ ሽሽት ፡ ይጠፋል ፥ ብርቱውም ፡ በብርታቱ ፡ አይበረታም ፥ ኀያሉም ፡ ነፍሱን ፡ አያድንም ፤

15 ፤ ቀስተኛውም ፡ አይቆምም ፥ ፈጣኑም ፡ አይድንም ፥ ፈረሰኛውም ፡ ነፍሱን ፡ አያድንም ፤

16 ፤ በኀያላኑም ፡ መካከል ፡ ልበ ፡ ሙሉው ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ዕራቍቱን ፡ ኾኖ ፡ ይሸሻል ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

ትንቢተ ፡ ዓሞጽ ፥ ምዕራፍ ፡ 3 ።

ምዕራፍ ፡ 3 ።

1 ፤ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፥ እግዚአብሔር ፡ በእናንተ ፥ ከግብጽ ፡ ምድር ፡ ባወጣኹት ፡ ወገን ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፡ የተናገረውን ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ስሙ ፤

2 ፤ እንዲህም ፡ ብሏል ፦ እኔ ፡ ከምድር ፡ ወገን ፡ ኹሉ ፡ እናንተን ፡ ብቻችኹን ፡ ዐውቄያችኋለኹ ፤ ስለዚህ ፥ ስለ ፡ ኀጢአታችኹ ፡ ኹሉ ፡ እበቀላችኋለኹ ።

3 ፤ በእውኑ ፡ ኹለት ፡ ሰዎች ፡ ሳይስማሙ ፡ በአንድነት ፡ ይኼዳሉን ፧

4 ፤ ወይስ ፡ አንበሳ ፡ የሚነጥቀው ፡ ነገር ፡ ሳያገኝ ፡ በጫካ ፡ ውስጥ ፡ ያገሣልን ፧ ወይስ ፡ የአንበሳ ፡ ደቦል ፡ አንዳች ፡ ሳይዝ ፡ በመደቡ ፡ ኾኖ ፡ ይጮኻልን ፧

5 ፤ ወይስ ፡ ወፍ ፥ አጥማጅ ፡ ከሌለው ፥ በምድር ፡ ላይ ፡ በወጥመድ ፡ ይያዛልን ፧ ወይስ ፡ ወስፈንጠር ፡ አንዳች ፡ ሳይዝ ፡ ከምድር ፡ ይፈነጠራልን ፧

6 ፤ ወይስ ፡ በከተማ ፡ ውስጥ ፡ መለከት ፡ ሲነፋ ፡ ሕዝቡ ፡ አይፈራምን ፧ ወይስ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ በከተማ ፡ ላይ ፡ የመጣ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ ያደረገው ፡ እግዚአብሔር ፡ አይደለምን ፧

7 ፤ በእውነት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ምስጢሩን ፡ ለባሪያዎቹ ፡ ለነቢያት ፡ ካልነገረ ፡ በቀር ፡ ምንም ፡ አያደርግም ።

8 ፤ አንበሳው ፡ አገሣ ፤ የማይፈራ ፡ ማን ፡ ነው ፧ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተናገረ ፤ ትንቢት ፡ የማይናገር ፡ ማን ፡ ነው ፧

9 ፤ በአዛጦን ፡ አዳራሾችና ፡ በግብጽ ፡ ምድር ፡ አዳራሾች ፡ አውሩና ፦ በሰማርያ ፡ ተራራዎች ፡ ላይ ፡ ተሰብሰቡ ፥ በውስጧም ፡ የኾነውን ፡ ታላቁን ፡ ውካታ ፥ በመካከሏም ፡ ያለውን ፡ ግፍ ፡ ተመልከቱ ፡ በሉ ።

10 ፤ ግፍንና ፡ ቅሚያን ፡ በአዳራሾቻቸው ፡ የሚያከማቹት ፡ ቅን ፡ ነገርን ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ አያውቁም ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

11 ፤ ስለዚህ ፥ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ በምድሪቱ ፡ ዙሪያ ፡ ጠላት ፡ ይመጣል ፤ ብርታትሽንም ፡ ከአንቺ ፡ ያወርዳል ፥ አዳራሾችሽም ፡ ይበዘበዛሉ ።

12 ፤ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ እረኛ ፡ ከአንበሳ ፡ አፍ ፡ ኹለት ፡ እግርን ፡ ወይም ፡ የጆሮን ፡ ጫፍ ፡ እንደሚያድን ፥ እንዲሁ ፡ በሰማርያ ፡ በዐልጋ ፡ ማእዘን ፥ በደማስቆም ፡ በምንጣፍ ፡ ላይ ፡ የተቀመጡት ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ይድናሉ ።

13 ፤ ስሙ ፥ በያዕቆብም ፡ ቤት ፡ ላይ ፡ መስክሩ ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ አምላክ ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

14 ፤ እስራኤልን ፡ ስለ ፡ ኀጢአቱ ፡ በምበቀልበት ፡ ቀን ፡ የቤቴልን ፡ መሠዊያዎች ፡ ደግሞ ፡ እበቀላለኹ ፤ የመሠዊያው ፡ ቀንዶች ፡ ይሰበራሉ ፥ ወደ ፡ ምድርም ፡ ይወድቃሉ ።

15 ፤ የክረምቱንና ፡ የበጋውን ፡ ቤት ፡ እመታለኹ ፤ በዝኆንም ፡ ጥርስ ፡ የተለበጡት ፡ ቤቶች ፡ ይጠፋሉ ፥ ታላላቆችም ፡ ቤቶች ፡ ይፈርሳሉ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

ትንቢተ ፡ ዓሞጽ ፥ ምዕራፍ ፡ 4 ።

ምዕራፍ ፡ 4 ።

1 ፤ በሰማርያ ፡ ተራራ ፡ የምትኖሩ ፥ ድኻዎችንም ፡ የምትበድሉ ፥ ችጋረኛዎችንም ፡ የምታስጨንቁ ፥ ጌታዎቻቸውንም ፦ አምጡ ፡ እንጠጣ ፡ የምትሉ ፡ እናንተ ፡ የባሳን ፡ ላሞች ፡ ሆይ ፥ ይህን ፡ ቃል ፡ ስሙ ።

2 ፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፦ እናንተን ፡ በሰልፍ ፡ ዕቃ ፥ ቅሬታችኹንም ፡ በመቃጥን ፡ የሚወስዱበት ፡ ቀን ፥ እንሆ ፥ በላያችኹ ፡ ይመጣል ፡ ብሎ ፡ በቅዱስነቱ ፡ ምሏል ።

3 ፤ እያንዳንዳችኹ ፡ በየፊታችኹ ፡ በተነደለ ፡ ስፍራ ፡ ትወጣላችኹ ፤ በሬማንም ፡ ትጣላላችኹ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

4 ፤ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፥ ይህን ፡ ወዳችኋልና ፥ ወደ ፡ ቤቴል ፡ ኑና ፡ ኀጢአትን ፡ ሥሩ ፤ ወደ ፡ ገልገላ ፡ ኑና ፡ ኀጢአትን ፡ አብዙ ፤ በየማለዳውም ፡ መሥዋዕታችኹን ፥ በየሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ ዐሥራታችኹን ፡ አቅርቡ ፤

5 ፤ ርሾ ፡ ካለበትም ፡ የምስጋናውን ፡ መሥዋዕት ፡ አቅርቡ ፥ በፈቃዳችኹም ፡ የምታቀርቡትን ፡ ዐውጁና ፡ አውሩ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

6 ፤ በከተማችኹ ፡ ኹሉ ፡ ጥርስን ፡ ማጥራት ፥ በስፍራችኹም ፡ ኹሉ ፡ እንጀራን ፡ ማጣት ፡ ሰጠኋችኹ ፤ እናንተ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አልተመለሳችኹም ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

7 ፤ መከር ፡ ሳይደርስ ፡ ገና ፡ ከሦስት ፡ ወር ፡ በፊት ፡ ዝናብ ፡ ከለከልኋችኹ ፤ በአንድም ፡ ከተማ ፡ ላይ ፡ አዘነብኹ ፥ በሌላውም ፡ ከተማ ፡ ላይ ፡ እንዳይዘንብ ፡ አደረግኹ ፤ ባንድ ፡ ወገን ፡ ዘነበ ፥ ያልዘነበበትም ፡ ወገን ፡ ደረቀ ።

8 ፤ የኹለት ፡ ወይም ፡ የሦስት ፡ ከተማዎች ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ አንዲት ፡ ከተማ ፡ ውሃ ፡ ይጠጡ ፡ ዘንድ ፡ ኼዱ ፥ ነገር ፡ ግን ፥ አልረኩም ፤ እናንተ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አልተመለሳችኹም ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

9 ፤ በዋግና ፡ በዐረማሞ ፡ መታኋችኹ ፤ የአታክልታችኹንም ፡ ብዛት ፡ ወይኖቻችኹንም ፡ በለሶቻችኹንም ፡ ወይራዎቻችኹንም ፡ ተምች ፡ በልቷል ፤ እናንተ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አልተመለሳችኹም ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

10 ፤ በግብጽ ፡ እንደ ፡ ነበረው ፡ ቸነፈርን ፡ ሰደድኹባችኹ ፤ ጕበዛዝታችኹን ፡ በሰይፍ ፡ ገደልኹ ፥ ፈረሶቻችኹንም ፡ አስማረክኹ ፤ የሰፈራችኹንም ፡ ግማት ፡ ወደ ፡ አፍንጫችኹ ፡ አወጣኹ ፤ እናንተ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አልተመለሳችኹም ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

11 ፤ ሰዶምንና ፡ ገሞራን ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ገለበጣቸው ፥ እንዲሁ ፡ ገለበጥኋችኹ ፥ እናንተም ፡ ከእሳት ፡ ውስጥ ፡ እንደ ፡ ተነጠቀ ፡ ትንታግ ፡ ኾናችኹ ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ወደ ፡ እኔ ፡ አልተመለሳችኹም ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

12 ፤ ስለዚህ ፥ እስራኤል ፡ ሆይ ፥ እንደዚህ ፡ አደርግብኻለኹ ፤ እስራኤልም ፡ ሆይ ፥ እንደዚህ ፡ ስለማደርግብኽ ፡ አምላክኽን ፡ ለመገናኘት ፡ ተዘጋጅ ።

13 ፤ እንሆ ፥ ተራራዎችን ፡ የሠራ ፥ ነፋስንም ፡ የፈጠረ ፥ የልቡንም ፡ ዐሳብ ፡ ለሰው ፡ የሚነግር ፥ ንጋትን ፡ ጨለማ ፡ የሚያደርግ ፥ በምድርም ፡ ከፍታዎች ፡ ላይ ፡ የሚረግጥ ፥ ስሙ ፡ የሰራዊት ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ።

____________________ትንቢተ ፡ ዓሞጽ ፥ ምዕራፍ ፡ 5 ። ____________________

ምዕራፍ ፡ 5 ።

1 ፤ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ፥ በእናንተ ፡ ላይ ፡ ለሙሾ ፡ የማነሣውን ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ስሙ ።

2 ፤ የእስራኤል ፡ ድንግል ፡ ወደቀች ፥ ከእንግዲህም ፡ ወዲህ ፡ አትነሣም ፤ በምድሯ ፡ ላይ ፡ ተጣለች ፥ የሚያስነሣትም ፡ የለም ።

3 ፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፦ ሺሕ ፡ ከሚወጣባት ፡ ከተማ ፡ መቶ ፡ ይቀርላታል ፥ መቶም ፡ ከሚወጣባት ፡ ከተማ ፡ ለእስራኤል ፡ ቤት ፡ ዐሥር ፡ ይቀርላታል ።

4 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ለእስራኤል ፡ ቤት ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፦ እኔን ፡ ፈልጉ ፥ በሕይወትም ፡ ትኖራላችኹ ፤

5 ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ገልገላ ፡ ፈጽሞ ፡ ትማረካለችና ፥ ቤቴልም ፡ ከንቱ ፡ ትኾናለችና ፡ ቤቴልን ፡ አትፈልጉ ፥ ወደ ፡ ገልገላም ፡ አትግቡ ፥ ወደ ፡ ቤርሳቤሕም ፡ አትለፉ ።

6 ፤ በዮሴፍ ፡ ቤት ፡ እሳት ፡ እንዳትቃጠል ፥ በቤቴል ፡ የሚያጠፋትም ፡ ሳይኖር ፡ እንዳትበላ ፥ እግዚአብሔርን ፡ ፈልጉ ፥ በሕይወትም ፡ ትኖራላችኹ ።

7 ፤ ፍርድን ፡ ወደ ፡ ሬት ፡ የምትለውጡ ፥ ጽድቅንም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ የምትጥሉ ፡ እናንተ ፡ ሆይ ፥

8 ፤ ሰባቱን ፡ ከዋክብትና ፡ ኦሪዮን ፡ የተባለውን ፡ ኮከብ ፡ የፈጠረውን ፥ የሞትን ፡ ጥላ ፡ ወደ ፡ ንጋት ፡ የሚለውጠውን ፥ ቀኑንም ፡ በሌሊት ፡ የሚያጨልመውን ፥ የባሕሩንም ፡ ውሃዎች ፡ ጠርቶ ፡ በምድር ፡ ፊት ፡ ላይ ፡ የሚያፈሳቸውን ፥

9 ፤ ዐምባውም ፡ እንዲፈርስ ፡ በብርቱ ፡ ላይ ፡ የድንገት ፡ ጥፋት ፡ የሚያመጣውን ፡ ፈልጉ ፤ ስሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ።

10 ፤ በበሩ ፡ አደባባይ ፡ የሚገሥጸውን ፡ ጠሉ ፥ እውነትም ፡ የሚናገረውን ፡ ተጸየፉ ።

11 ፤ ድኻውንም ፡ ደብድባችኋልና ፥ የስንዴውንም ፡ ቀረጥ ፡ ከርሱ ፡ ወስዳችኋልና ፥ ከተጠረበ ፡ ድንጋይ ፡ ቤቶችን ፡ ሠርታችኋል ፥ ነገር ፡ ግን ፥ አትቀመጡባቸውም ፤ ያማሩ ፡ የወይን ፡ ቦታዎች ፡ ተክላችኋል ፥ ነገር ፡ ግን ፥ ከወይን ፡ ጠጃቸው ፡ አትጠጡም ።

12 ፤ ጻድቁን ፡ የምታስጨንቁ ፥ ጉቦንም ፡ የምትቀበሉ ፥ በበሩም ፡ አደባባይ ፡ የችጋረኛውን ፡ ፍርድ ፡ የምታጣምሙ ፡ እናንተ ፡ ሆይ ፥ በደላችኹ ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ በዛ ፥ ኀጢአታችኹም ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ጸና ፡ እኔ ፡ ዐውቃለኹና ።

13 ፤ ስለዚህ ፥ ክፉ ፡ ዘመን ፡ ነውና ፥ በዚያ ፡ ዘመን ፡ አስተዋይ ፡ የሚኾን ፡ ዝም ፡ ይላል ።

14 ፤ በሕይወት ፡ ትኖሩ ፡ ዘንድ ፡ መልካሙን ፡ እንጂ ፡ ክፉውን ፡ አትፈልጉ ፤ እንዲህም ፡ እናንተ ፡ እንደ ፡ ተናገራችኹ ፡ የሰራዊት ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከእናንተ ፡ ጋራ ፡ ይኾናል ።

15 ፤ ክፉውን ፡ ጥሉ ፥ መልካሙንም ፡ ውደዱ ፥ በበሩም ፡ አደባባይ ፡ ፍርድን ፡ አጽኑ ፤ ምናልባት ፡ የሰራዊት ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለዮሴፍ ፡ ቅሬታ ፡ ይራራ ፡ ይኾናል ።

16 ፤ ስለዚህ ፥ ጌታ ፡ የሰራዊት ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ በያደባባዩ ፡ ዅሉ ፡ ላይ ፡ ዋይታ ፡ ይኾናል ፤ በየመንገዱም ፡ ዅሉ ፡ ላይ ፡ ወዮ ፡ ወዮ ፡ ይባላል ፤ ገበሬዎቹም ፡ ወደ ፡ ልቅሶ ፥ አልቃሾቹም ፡ ወደ ፡ ዋይታ ፡ ይጠራሉ ።

17 ፤ በመካከልኽ ፡ ዐልፋለኹና ፡ በወይኑ ፡ ቦታ ፡ ዅሉ ፡ ልቅሶ ፡ ይኾናል ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

18 ፤ የእግዚአብሔርን ፡ ቀን ፡ ለምትፈልጉ ፡ ወዮላችኹ! የእግዚአብሔርን ፡ ቀን ፡ ለምን ፡ ትፈልጋላችኹ ፧ ጨለማ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ብርሃን ፡ አይደለም ።

19 ፤ ከአንበሳ ፡ ፊት ፡ እንደ ፡ ሸሸ ፡ ድብም ፡ እንዳገኘው ፡ ሰው ፥ ወይም ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ ገብቶ ፡ እጁን ፡ በግድግዳ ፡ ላይ ፡ እንዳስደገፈና ፡ እባብ ፡ እንደ ፡ ነደፈው ፡ ሰው ፡ ነው ።

20 ፤ የእግዚአብሔር ፡ ቀን ፡ ብርሃን ፡ ሳይኾን ፡ ጨለማ ፡ አይደለምን ፧ ጸዳል ፡ የሌለውም ፡ ድቅድቅ ፡ ጨለማ ፡ አይደለምን ፧

21 ፤ ዓመት ፡ በዓላችኹን ፡ ጠልቼዋለኹ ፡ ተጸይፌውማለኹ ፤ የተቀደሰውም ፡ ጉባኤያችኹ ፡ ደስ ፡ አያሠኘኝም ።

22 ፤ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕታችኹና ፡ የእኽሉን ፡ ቍርባናችኹን ፡ ብታቀርቡልኝም ፡ እንኳ ፡ አልቀበለውም ፤ ለምስጋና ፡ መሥዋዕት ፡ የምታቀርቡልኝን ፡ የሰቡትን ፡ እንስሳዎች ፡ አልመለከትም ።

23 ፤ የዝማሬኽንም ፡ ጩኸት ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ አርቅ ፤ የመሰንቆኽንም ፡ ዜማ ፡ አላደምጥም ።

24 ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ፍርድ ፡ እንደ ፡ ውሃ ፥ ጽድቅም ፡ እንደማይደርቅ ፡ ፈሳሽ ፡ ይፍሰስ ።

25 ፤ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ፥ በእውኑ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ አርባ ፡ ዓመት ፡ ሙሉ ፡ መሥዋዕትንና ፡ ቍርባንን ፡ አቅርባችኹልኛልን ፧

26 ፤ ለራሳችኹም ፡ የሠራችኋቸውን ፡ ምስሎች ፥ የሞሎክን ፡ ድንኳንና ፡ የአምላካችኹን ፡ የሬፋን ፡ ኮከብ ፡ አነሣችኹ ።

27 ፤ ስለዚህ ፥ ከደማስቆ ፡ ወደዚያ ፡ አስማርካችኋለኹ ፥ ይላል ፡ ስሙ ፡ የሰራዊት ፡ አምላክ ፡ የተባለ ፡ እግዚአብሔር ።

____________________ትንቢ.ተ ፡ ዓሞጽ ፥ ምዕራፍ ፡ 6 ። ____________________

ምዕራፍ ፡ 6 ።

1 ፤ በጽዮን ፡ ላሉ ፡ ዓለመኛዎች ፥ በሰማርያም ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ተዘልለው ፡ ለተቀመጡ ፥ የእስራኤልም ፡ ቤት ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ለመጡባቸው ፡ ለአሕዛብ ፡ አለቃዎች ፡ ወዮላቸው!

2 ፤ ወደ ፡ ካልኔ ፡ ዐልፋችኹ ፡ ተመልከቱ ፤ ከዚያም ፡ ወደ ፡ ታላቂቱ ፡ ሐማት ፡ ኺዱ ፤ ከዚያም ፡ ወደ ፡ ፍልስጥኤም ፡ ጌት ፡ ውረዱ ፤ እነርሱ ፡ ከነዚህ ፡ መንግሥታት ፡ ይሻላሉን ፧ ወይስ ፡ ድንበራቸው ፡ ከድንበራችኹ ፡ ይሰፋልን ፧

3 ፤ ክፉውን ፡ ቀን ፡ ከእናንተ ፡ ለምታርቁ ፥ የግፍንም ፡ ወንበር ፡ ለምታቀርቡ ፥

4 ፤ ከዝኆን ፡ ጥርስ ፡ በተሠራ ፡ ዐልጋ ፡ ላይ ፡ ለምትተኙ ፥ በምንጣፋችኹም ፡ ላይ ፡ ተደላድላችኹ ፡ ለምትቀመጡ ፥ ከበጎችም ፡ መንጋ ፡ ጠቦትን ፡ ከጋጥም ፡ ውስጥ ፡ ጥጃን ፡ ለምትበሉ ፥

5 ፤ በመሰንቆም ፡ ድምፅ ፡ ለምትንጫጩ ፥ እንደ ፡ ዳዊትም ፡ የዜማን ፡ ዕቃ ፡ ለምታዘጋጁ ፥

6 ፤ በፋጋ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ለምትጠጡ ፥ እጅግ ፡ ባማረ ፡ ሽቱም ፡ ለምትቀቡ ፥ ስለዮሴፍ ፡ መከራ ፡ ግን ፡ ለማታዝኑ ፡ ለእናንተ ፡ ወዮላችኹ!

7 ፤ ስለዚህ ፥ በምርኮ ፡ መገምሪያ ፡ ይማረካሉ ፥ ተደላድለው ፡ ከተቀመጡትም ፡ ዘንድ ፡ ዘፈን ፡ ይርቃል ።

8 ፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፦ የያዕቆብን ፡ ትዕቢት ፡ ተጸይፌያለኹ ፥ አዳራሾቹንም ፡ ጠልቻለኹ ፤ ስለዚህ ፥ ከተማዪቱንና ፡ የሚኖሩባትን ፡ ዅሉ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጣለኹ ፡ ብሎ ፡ በራሱ ፡ ምሏል ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ።

9 ፤ እንዲህም ፡ ይኾናል ፤ ዐሥር ፡ ሰዎች ፡ ባንድ ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ ቢቀሩ ፡ እነርሱ ፡ ይሞታሉ ።

10 ፤ ዐጥንቱንም ፡ ከቤቱ ፡ ያወጡ ፡ ዘንድ ፡ የሰው ፡ ዘመድና ፡ አቃጣዩ ፡ ባነሡት ፡ ጊዜ ፥ በቤቱም ፡ ውስጥ ፡ ያለውን ፦ እስከ ፡ አኹን ፡ ድረስ ፡ ገና ፡ ሰው ፡ ባንተ ፡ ዘንድ ፡ አለን ፧ ባለው ፡ ጊዜ ፥ ርሱም ፦ ማንም ፡ የለም ፡ ባለ ፡

ጊዜ ፤ ያን ፡ ጊዜ ፦ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ እንጠራ ፡ ዘንድ ፡ አይገባንምና ፥ ዝም ፡ በል ፡ ይለዋል ።

11 ፤ እንሆም ፥ እግዚአብሔር ፡ ያዛል ፤ ታላቁንም ፡ ቤት ፡ በማፍረስ ፥ ታናሹንም ፡ ቤት ፡ በመሰባበር ፡ ይመታል ።

12 ፤ 13 ፤ ፍርድን ፡ ወደ ፡ ሐሞት ፥ የጽድቅንም ፡ ፍሬ ፡ ወደ ፡ ሬት ፡ የለወጣችኹ ፥ በከንቱም ፡ ነገር ፡ ደስ ፡
የሚላችኹ ፦ በኀይላችን ፡ ቀንድ ፡ የወሰድን ፡ አይደለምን ፥ የምትሉ ፥ እናንተ ፡ ሆይ ፥ በእውኑ ፡ ፈረሶች ፡ በጭንጫ ፡
ላይ ፡ ይጋልባሉን ፥ ወይስ ፡ በሬዎች ፡ በዚያ ፡ ላይ ፡ ያርሳሉን ፥

14 ፤ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ፥ እንሆ ፥ እኔ ፡ ሕዝብን ፡ አስነሣባችኋለኹ ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ አምላክ ፡
እግዚአብሔር ፤ እነርሱም ፡ ከሐማት ፡ መግቢያ ፡ ዠምረው ፡ እስከዐረባ ፡ ወንዝ ፡ ድረስ ፡ ያስጨንቋችኋል ።

## ___ትንቢተ ፡ ዓሞጽ ፥ ምዕራፍ ፡ 7 ። ___

ምዕራፍ ፡ 7 ።

1 ፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ አሳየኝ ፤ እንሆም ፥ የኋለኛው ፡ ሣር ፡ በሚበቅልበት ፡ መዠመሪያ ፡ ላይ ፡ አንበጣን ፡
ፈጠረ ፤ እንሆም ፥ ከንጉሡ ፡ ዐጨዳ ፡ በኋላ ፡ የበቀለ ፡ የገቦ ፡ ነበረ ።

2 ፤ የምድሩንም ፡ ሣር ፡ በልተው ፡ ከጨረሱ ፡ በኋላ ፥ እኔ ፦ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፥ ይቅር ፡ እንድትል ፡
እለምንኻለኹ ፤ ያዕቆብ ፡ ታናሽ ፡ ነውና ፥ እንዴት ፡ ይቆማል ፥ አልኹ ።

3 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ተጸጸተ ፤ ይህ ፡ አይኾንም ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

4 ፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡ እንዲህ ፡ አሳየኝ ፤ እንሆም ፥ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእሳት ፡ ለመፍረድ ፡ ጠራ ፤ ርሷም ፡
ታላቁን ፡ ቀላይና ፡ ምድርን ፡ በላች ።

5 ፤ እኔም ፦ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፥ እንድትተው ፡ እለምንኻለኹ ፤ ያዕቆብ ፡ ታናሽ ፡ ነውና ፥ እንዴት ፡
ይቆማል ፥ አልኹ ።

6 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ተጸጸተ ፤ ይህ ፡ ደግሞ ፡ አይኾንም ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

7 ፤ እንዲህም ፡ አሳየኝ ፤ እንሆም ፥ ጌታ ፡ ቱንቢውን ፡ ይዞ ፡ በቱንቢ ፡ በተሠራ ፡ ቅጥር ፡ ላይ ፡ ቆሞ ፡ ነበር ።

8 ፤ እግዚአብሔርም ፦ ዓሞጽ ፡ ሆይ ፥ የምታየው ፡ ምንድር ፡ ነው ፥ አለኝ ። እኔም ፦ ቱንቢ ፡ ነው ፡
አልኹ ። ጌታም ፦ እንሆ ፥ በሕዝቤ ፡ በእስራኤል ፡ መካከል ፡ ቱንቢ ፡ አደርጋለኹ ፤ ከእንግዲህም ፡ ወዲህ ፡ ደግሞ ፡
አላልፋቸውም ፤

9 ፤ የይሥሐቅም ፡ የኰረብታው ፡ መስገጃዎች ፡ ይፈርሳሉ ፥ የእስራኤልም ፡ መቅደሶች ፡ ባድማ ፡
ይኾናሉ ፤ በኢዮርብዓምም ፡ ቤት ፡ ላይ ፡ በሰይፍ ፡ እነሣለኹ ፡ አለ ።

10 ፤ 11 ፤ የቤቴልም ፡ ካህን ፡ አሜስያስ ፡ ወደእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ወደ ፡ ኢዮርብዓም ፡ ልኮ ፦ ዓሞጽ ፦ ኢዮርብዓም ፡
በሰይፍ ፡ ይሞታል ፥ እስራኤልም ፡ ከአገሩ ፡ ተማርኮ ፡ ይኼዳል ፡ ብሏልና ፥ ዓሞጽ ፡ በእስራኤል ፡ ቤት ፡ መካከል ፡
ዐምፆብኻል ፤ ምድሪቱም ፡ ቃሉን ፡ ኹሉ ፡ ልትሸከም ፡ አትችልም ፡ አለ ።

12 ፤ አሜስያስም ፡ ዓሞጽን ፦ ባለራእዩ ፡ ሆይ ፥ ኺድ ፡ ወደይሁዳም ፡ ምድር ፡ ሽሽ ፥ በዚያም ፡ እንጀራን ፡ ብላ ፥

13 ፤ በዚያም ፡ ትንቢትን ፡ ተናገር ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ቤቴል ፡ የንጉሥ ፡ መቅደስና ፡ የመንግሥት ፡ ቤት ፡ ናትና ፥ ከእንግዲህ ፡
ወዲህ ፡ በዚህ ፡ ደግሞ ፡ ትንቢት ፡ አትናገር ፡ አለው ።

14 ፤ ዓሞጽም ፡ መልሶ ፡ አሜስያስን ፡ አለው ፦ እኔ ፡ ላም ፡ ጠባቂና ፡ ወርካ ፡ ለቃሚ ፡ ነኝ ፡ እንጂ ፡ ነቢይ ፡ ወይም ፡
የነቢይ ፡ ልጅ ፡ አይደለኹም ፤

15 ፤ እግዚአብሔርም ፡ በጎቹን ፡ ከመከተል ፡ ወሰደኝ ፥ እግዚአብሔርም ፦ ኺድ ፥ ለሕዝቤም ፡ ለእስራኤል ፡ ትንቢት ፡
ተናገር ፡ አለኝ ።

16 ፤ አኹንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስማ ፤ አንተ ፦ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ትንቢት ፡ አትናገር ፥ በይሥሐቅም ፡ ቤት ፡
ላይ ፡ አትስበክ ፡ ብለኻል ፤

17 ፤ ስለዚህ ፥ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ሚስትኽ ፡ በከተማዪቱ ፡ ውስጥ ፡ ጋለሞታ ፡ ትኾናለች ፥ ወንዶችና ፡
ሴቶች ፡ ልጆችኽም ፡ በሰይፍ ፡ ይወድቃሉ ፥ ምድርኽም ፡ በገመድ ፡ ትከፈላለች ፤ አንተም ፡ በረከሰች ፡ ምድር ፡
ትሞታለኽ ፥ እስራኤልም ፡ ከምድሩ ፡ ተማርኮ ፡ ይኼዳል ።

ትንቢተ ፡ ዓሞጽ ፥ ምዕራፍ ፡ 8 ።

ምዕራፍ ፡ 8 ።

1 ፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ አሳየኝ ፡ እንሆም ፥ የቃርሚያ ፡ ፍሬ ፡ የሞላበት ፡ እንቅብ ፡ ነበረ ።

2 ፤ ርሱም ፦ ዓሞጽ ፡ ሆይ ፥ የምታየው ፡ ምንድር ፡ ነው ፡ አለኝ ። እኔም ፦ የቃርሚያ ፡ ፍሬ ፡ የሞላበት ፡ እንቅብ ፡
ነው ፡ አልኹት ። እግዚአብሔርም ፡ አለኝ ፦ ፍጻሜ ፡ በሕዝቤ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ መጥቷል ፤ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡
ደግሞ ፡ አላልፋቸውም ።

3 ፤ የመቅደሱ ፡ ዝማሬ ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ዋይታ ፡ ይኾናል ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ የሰዎችም ፡ ሬሳ ፡
ይበዛል ፥ በስፍራውም ፡ ኹሉ ፡ በዝምታ ፡ ይጣላል ።

4 ፤ ችጋረኛውን ፡ የምትውጡ ፥ የአገሩንም ፡ ድኻ ፡ የምታጠፉ ፡ እናንተ ፡ ሆይ ፦

5 ፤ እኽልን ፡ እንሸጥ ፡ ዘንድ ፡ መባቻው ፡ መቼ ፡ ያልፋል ፤ የኢፍ ፡ መስፈሪያውንም ፡ እያሳነስን ፥ ሰቅሉንም ፡
እያበዛን ፥ በሐሰተኛም ፡ ሚዛን ፡ እያታለልን ፥

6 ፤ ድኻውን ፡ በብር ፡ ችጋረኛውንም ፡ ባንድ ፡ ጥንድ ፡ ጫማ ፡ እንገዛ ፡ ዘንድ ፥ የስንዴውን ፡ ግርድ ፡ እንሸጥ ፡ ዘንድ ፡
ስንዴውን ፡ እንድንሸምት ፡ ሰንበት ፡ መቼ ፡ ያልፋል ፤ የምትሉ ፡ እናንተ ፡ ሆይ ፥ ይህን ፡ ስሙ ።

7 ፤ እግዚአብሔር ፡ በያዕቆብ ፡ ክብር ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ምሏል ። ሥራቸውን ፡ ኹሉ ፡ ለዘለዓለም ፡ ምንም ፡ አልረሳም ።

8 ፤ በእውኑ ፡ ምድሪቱ ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ አትናወጥምን ፤ በርሷም ፡ የሚኖር ፡ ኹሉ ፡ አያለቅስምን ፤ መላዋም ፡ እንደ ፡
ወንዙ ፡ ትነሣለች ፤ እንደ ፡ ግብጽም ፡ ወንዝ ፡ ትነሣለች ፡ ደግሞም ፡ ትወርዳለች ።

9 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ ፀሓይ ፡ በቀትር ፡ እንድትገባ ፡ አደርጋለኹ ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ በብርሃንም ፡ ቀን ፡
ምድሩን ፡ አጨልማለኹ ።

10 ፤ ዓመት ፡ በዓላችኹንም ፡ ወደ ፡ ልቅሶ ፥ ዝማሬያችኹንም ፡ ወደ ፡ ዋይታ ፡ እለውጣለኹ ፤ ማቅንም ፡ በወገብ ፡
ኹሉ ፥ ራስ ፡ መንጨትንም ፡ በኹሉ ፡ ላይ ፡ አመጣለኹ ፤ እንደ ፡ አንድያ ፡ ልጅም ፡ ልቅሶ ፥ ፍጻሜውንም ፡ እንደ ፡
መራራ ፡ ቀን ፡ አደርገዋለኹ ።

11 ፤ እንሆ ፥ በምድር ፡ ላይ ፡ ራብን ፡ የምሰድበት ፡ ዘመን ፡ ይመጣል ፥ ይላል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ ርሱም ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ከመስማት ፡ እንጂ ፡ እንጀራን ፡ ከመራብና ፡ ውሃን ፡ ከመጠማት ፡ አይደለም ።

12 ፤ ከባሕርም ፡ እስከ ፡ ባሕር ፡ ድረስ ፥ ከሰሜንም ፡ እስከ ፡ ምሥራቅ ፡ ድረስ ፡ ይቅበዘበዛሉ ፤ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡
ለመሻት ፡ ይሯሯጣሉ ፥ አያገኙትምም ።

13 ፤ በዚያ ፡ ቀን ፡ መልካካሞች ፡ ደናግል ፡ ጕበዛዝትም ፡ በጥም ፡ ይዝላሉ ።

14 ፤ በሰማርያ ፡ ኀጢአት ፡ የሚምሉና ፦ ዳን ፡ ሆይ ፥ ሕያው ፡ አምላክኽን! ደግሞ ፦ ሕያው ፡ የቤርሳቤሕን ፡ መንገድ!
ብለው ፡ የሚሉ ፥ እነርሱ ፡ ይወድቃሉ ፥ ደግሞም ፡ አይነሡም ።

ትንቢተ ፡ ዓሞጽ ፥ ምዕራፍ ፡ 9 ።

ምዕራፍ ፡ 9 ።

1 ፤ ጌታን ፡ በመሠዊያው ፡ አጠገብ ፡ ቆሞ ፡ አየኹት ፤ ርሱም ፡ እንዲህ ፡ አለ ፦ መድረኮቹ ፡ ይናወጡ ፡ ዘንድ ፡
ጕልላቶቹን ፡ ምታ ፥ በራሳቸውም ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፡ ሰባብራቸው ፤ እኔም ፡ ከነርሱ ፡ የቀሩትን ፡ በሰይፍ ፡
እገድላለኹ ፤ የሚሸሽ ፡ አያመልጥም ፥ የሚያመልጥም ፡ አይድንም ።

2 ፤ ወደ ፡ ሲኦል ፡ ቢወርዱ ፡ እጄ ፡ ከዚያ ፡ ታወጣቸዋለች ፤ ወደ ፡ ሰማይም ፡ ቢወጡ ፡ ከዚያ ፡ አወርዳቸዋለኹ ፤

3 ፤ በቀርሜሎስም ፡ ራስ ፡ ውስጥ ፡ ቢሸሸጉ ፡ ፈልጌ ፡ ከዚያ ፡ አወጣቸዋለኹ ፤ በጥልቅ ፡ ባሕርም ፡ ውስጥ ፡ ከዐይኔ ፡ ቢደበቁ ፡ ከዚያ ፡ እባቡን ፡ አዝዛለኹ ፥ ርሱም ፡ ይነድፋቸዋል ፤

4 ፤ በጠላቶቻቸውም ፡ ፊት ፡ ተማርከው ፡ ቢኼዱ ፡ ከዚያ ፡ ሰይፍን ፡ አዝዛለኹ ፥ ርሱም ፡ ይገድላቸዋል ፤ ዐይኔንም ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ለክፋት ፡ እንጂ ፡ ለመልካም ፡ አላደርግም ።

5 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ምድርን ፡ ይዳስሳል ፡ ርሷም ፡ ትቀልጣለች ፥ የሚኖሩባትም ፡ ዅሉ ፡ ያለቅሳሉ ፤ መላዋም ፡ እንደ ፡ ግብጽ ፡ ወንዝ ፡ ትነሣለች ፥ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ግብጽ ፡ ወንዝ ፡ ትወርዳለች ።

6 ፤ አዳራሹን ፡ በሰማይ ፡ የሠራ ፥ ጠፈሩንም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ የመሠረተ ፥ የባሕርንም ፡ ውሃ ፡ ጠርቶ ፡ በምድር ፡ ፊት ፡ ላይ ፡ የሚያፈሰው ፡ ርሱ ፡ ነው ፤ ስሙም ፡ እግዚአብሔር ፡ ነው ።

7 ፤ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፥ እናንተ ፡ ለእኔ ፡ እንደ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ልጆች ፡ አይደላችኹምን ፧ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤— እስራኤልን ፡ ከግብጽ ፡ ምድር ፥ ፍልስጥኤማውያንንም ፡ ከከፍቶር ፥ ሶርያውያንንም ፡ ከቂር ፡ አላወጣኹምን ፧

8 ፤ እንሆ ፥ የጌታ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ዐይኖች ፡ በኀጢአተኛ ፡ መንግሥት ፡ ላይ ፡ ናቸው ፥ ከምድርም ፡ ፊት ፡ አጠፋታለኹ ፤ ነገር ፡ ግን ፥ የያዕቆብን ፡ ቤት ፡ ፈጽሜ ፡ አላጠፋም ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

9 ፤ እንሆ ፥ አዝዛለኹ ፥ እኽልም ፡ በወንፊት ፡ እንዲነፋ ፡ የእስራኤልን ፡ ቤት ፡ በአሕዛብ ፡ ዅሉ ፡ መካከል ፡ እነፋለኹ ፤ ነገር ፡ ግን ፥ አንዲት ፡ ቅንጣት ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ አትወድቅም ።

10 ፤ ክፉው ፡ ነገር ፡ አይደርስብንም ፥ አያገኘንምም ፡ የሚሉ ፡ የሕዝቤ ፡ ኀጢአተኛዎች ፡ ዅሉ ፡ በሰይፍ ፡ ይሞታሉ ።

11 ፤ በዚያ ፡ ቀን ፡ የወደቀችውን ፡ የዳዊትን ፡ ድንኳን ፡ አነሣለኹ ፥ የተናደውንም ፡ ቅጥሯን ፡ እጠግናለኹ ፤ የፈረሰውንም ፡ ዐድሳለኹ ፥ እንደ ፡ ቀደመውም ፡ ዘመን ፡ እሠራታለኹ ፤

12 ፤ ይኸውም ፡ የኤዶምያስን ፡ ቅሬታ ፥ ስሜም ፡ የተጠራባቸውን ፡ አሕዛብን ፡ ዅሉ ፡ ይወርሱ ፡ ዘንድ ፡ ነው ፥ ይላል ፡ ይህን ፡ የሚያደርግ ፡ እግዚአብሔር ።

13 ፤ እንሆ ፥ አራሹ ፡ ዐጫጁን ፥ ወይን ፡ ጠማቂውም ፡ ዘሪውን ፡ የሚያገኝበት ፡ ወራት ፡ ይመጣል ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ ተራራዎችም ፡ በተሓውን ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ያንጠባጥባሉ ፥ ኰረብታዎችም ፡ ዅሉ ፡ ይቀልጣሉ ።

14 ፤ የሕዝቤን ፡ የእስራኤልን ፡ ምርኮ ፡ እመልሳለኹ ፥ የፈረሱትንም ፡ ከተማዎች ፡ ሠርተው ፡ ይቀመጡባቸዋል ፤ ወይንንም ፡ ይተክላሉ ፥ የወይን ፡ ጠጁንም ፡ ይጠጣሉ ፤ አታክልትንም ፡ ያበጃሉ ፥ ፍሬውንም ፡ ይበላሉ ።

15 ፤ በምድራቸውም ፡ እተክላቸዋለኹ ፥ ከእንግዲህም ፡ ወዲህ ፡ ከሰጠኍቸው ፡ ከምድራቸው ፡ አይነቀሉም ፥ ይላል ፡ አምላክኽ ፡ እግዚአብሔር ፨

# ትንቢተ ፡ ዐብድዩ ።

(ክለሳ.1.20020507)

ትንቢተ ፡ ዐብድዩ ፥ ምዕራፍ ፡ 1 ።

ምዕራፍ ፡ 1

1 ፤ የዐብድዩ ፡ ራእይ ፦ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ ኤዶምያስ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ወሬ ፡
ሰምተናል ፤ መልእክተኛ ፡ ወደ ፡ አሕዛብ ፡ ተልኮ ፦ ተነሡ ፥ በላይዋም ፡ በሰልፍ ፡ እንነሣ ፡ ብሏል ።

2 ፤ እንሆ ፥ በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ ታናሽ ፡ አድርጌኻለኹ ፤ አንተ ፡ እጅግ ፡ ተንቀኻል ።

3 ፤ በተሰነጠቀ ፡ አለት ፡ ውስጥ ፡ የምትኖር ፥ ማደሪያኽንም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደረግኽ ፥ በልብኽም ፦ ወደ ፡ ምድር ፡
የሚያወርደኝ ፡ ማን ፡ ነው ፡ የምትል ፡ አንተ ፡ ሆይ ፥ የልብኽ ፡ ትዕቢት ፡ አታሎኻል ።

4 ፤ እንደ ፡ ንስር ፡ መጥቀኽ ፡ ብትወጣ ፥ ቤትኽም ፡ በከዋክብት ፡ መካከል ፡ ቢኾን ፥ ከዚያ ፡ አወርድኻለኹ ፥ ይላል ፡
እግዚአብሔር ።

5 ፤ ሌባዎች ፡ ቢመጡብኽ ፡ ወይም ፡ ወንበዴዎች ፡ በሌሊት ፡ ቢመጡ ፥ የሚበቃቸውን ፡ የሚሰርቁ ፡
አይደሉምን ፡ ወይንንም ፡ የሚቈርጡ ፡ ወዳንተ ፡ ቢመጡ ፡ ቃርሚያ ፡ አያስቀሩምን ፡

6 ፤ አንተ ፡ ግን ፡ ምንኛ ፡ ጠፋኽ! ዔሳው ፡ ምንኛ ፡ ተመረመረ! የተሸሸገበት ፡ ነገር ፡ ምንኛ ፡ ተፈለገ!

7 ፤ የተማማልኻቸው ፡ ሰዎች ፡ ኹሉ ፡ ወደ ፡ ዳርቻኽ ፡ ሰደዱኽ ፤ የታመንኻቸው ፡ ሰዎች ፡
አታለሉኽ ፥ አሸነፉኽም ፤ በበታችኽም ፡ አሽክላ ፡ ዘረጉብኽ ፥ እነርሱም ፡ ማስተዋል ፡ የላቸውም ።

8 ፤ በዚያ ፡ ቀን ፡ ከኤዶምያስ ፡ ጥበበኛዎችን ፥ ከዔሳውም ፡ ተራራ ፡ ማስተዋልን ፡ አላጠፋምን ፡ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

9 ፤ ቴማን ፡ ሆይ ፥ ሰዎች ፡ ኹሉ ፡ ከዔሳው ፡ ተራራ ፡ በመገደል ፡ ይጠፉ ፡ ዘንድ ፡ ኀያላንኽ ፡ ይደነግጣሉ ።

10 ፤ በወንድምኽ ፡ በያዕቆብ ፡ ላይ ፡ ስለ ተደረገ ፡ ግፍ ፡ ዕፍረት ፡ ይከድንኻል ፥ ለዘለዓለምም ፡ ትጠፋለኽ ።

11 ፤ በፊቱ ፡ አንጻር ፡ በቆምኽ ፡ ቀን ፥ አሕዛብ ፡ ጭፍራውን ፡ በማረኩበት ፥ እንግዳዎችም ፡ በበሩ ፡
በገቡበት ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ ዕጣ ፡ በተጣጣሉበት ፡ ቀን ፡ አንተ ፡ ደግሞ ፡ ከነርሱ ፡ እንደ ፡ አንዱ ፡ ነበርኽ ።

12 ፤ ነገር ፡ ግን ፥ በመከራው ፡ ቀን ፡ ወንድምኽን ፡ ትመለከት ፡ ዘንድ ፥ በጥፋታቸውም ፡ ቀን ፡ በይሁዳ ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡
ደስ ፡ ይልኽ ፡ ዘንድ ፥ በጭንቀትም ፡ ቀን ፡ በትዕቢት ፡ ትናገር ፡ ዘንድ ፡ አይገባኽም ፡ ነበር ።

13 ፤ በጥፋታቸውም ፡ ቀን ፡ በሕዝቤ ፡ በር ፡ ትገባ ፡ ዘንድ ፥ በጥፋታቸውም ፡ ቀን ፡ መከራቸውን ፡ ትመለከት ፡
ዘንድ ፥ በጥፋታቸውም ፡ ቀን ፡ በሀብታቸው ፡ ላይ ፡ እጅኽን ፡ ትዘረጋ ፡ ዘንድ ፡ አይገባኽም ፡ ነበር ።

14 ፤ የሸሹትንም ፡ ለመግደል ፡ በመንታ ፡ መንገድ ፡ ላይ ፡ ትቆም ፡ ዘንድ ፥ በጭንቀትም ፡ ቀን ፡ ከርሱ ፡ የቀሩትን ፡
አሳልፈኽ ፡ ትሰጥ ፡ ዘንድ ፡ አይገባኽም ፡ ነበር ።

15 ፤ የእግዚአብሔር ፡ ቀን ፡ በአሕዛብ ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፡ ቀርቧልና ፤ አንተ ፡ እንዳደረግኸው ፡ እንዲሁ ፡
ይደረግብኻል ፥ ፍዳኽም ፡ በራስኽ ፡ ላይ ፡ ይመለሳል ።

16 ፤ በቅዱስ ፡ ተራራዬ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ጠጣችኹ ፡ እንዲሁ ፡ አሕዛብ ፡ ኹሉ ፡ ዘወትር ፡ ይጠጣሉ ፤ አዎን ፡
ይጠጣሉ ፥ ይጨልጡማል ፥ እንዳልኾኑም ፡ ይኾናሉ ።

17 ፤ ነገር ፡ ግን ፥ በጽዮን ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ የሚያመልጡ ፡ ይኾናሉ ፥ ርሱም ፡ ቅዱስ ፡ ይኾናል ፤ የያዕቆብም ፡ ቤት ፡
ሰዎች ፡ ርስታቸውን ፡ ይወርሳሉ ።

18 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ተናግሯልና ፥ የያዕቆብ ፡ ቤት ፡ እሳት ፥ የዮሴፍ ፡ ቤት ፡ ነበልባልም ፥ የዔሳው ፡ ቤት ፡ ገለባ ፡
ይኾናሉ ፤ እነርሱንም ፡ ያቃጥሏቸዋል ፡ ይበሏቸውማል ፤ ከዔሳውም ፡ ቤት ፡ ቅሬታ ፡ የለውም ።

19 ፤ የደቡብም ፡ ሰዎች ፡ የዔሳውን ፡ ተራራ ፥ የቈላውም ፡ ሰዎች ፡ ፍልስጥኤማውያንን ፡ ይወርሳሉ ፤ የኤፍሬምንም ፡
አገር ፡ የሰማርያንም ፡ አገር ፡ ይወርሳሉ ፤ ብንያምም ፡ ገለዓድን ፡ ይወርሳል ።

20 ፤ ይህም ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ የጭፍራቸው ፡ ምርኮ ፡ የከነዓንን ፡ ስፍራ ፡ ኹሉ ፡ እስከ ፡ ሰራጵታ ፡ ድረስ ፡
ይወርሳል ፤ በስፋራድም ፡ የሚኖሩ ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ምርኮኞች ፡ የደቡብን ፡ ከተማዎች ፡ ይወርሳሉ ።

21 ፤ በዔሳውም ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ይፈርዱ ፡ ዘንድ ፡ አዳኞች ፡ ወደጽዮን ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ይወጣሉ ፤ መንግሥቱም ፡
ለእግዚአብሔር ፡ ይኾናል ፨

# ትንቢተ ፡ ዮናስ ።

(ክለሳ.1.20020507)

## ትንቢተ ፡ ዮናስ ፥ ምዕራፍ ፡ 1 ።

ምዕራፍ ፡ 1 ።

1 ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደዐማቴ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ዮናስ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፦

2 ፤ ተነሥተኽ ፡ ወደዚያች ፡ ወደ ፡ ታላቂቱ ፡ ከተማ ፡ ወደ ፡ ነነዌ ፡ ኺድ ፥ ክፋታቸውም ፡ ወደ ፡ ፊቴ ፡
ወጥቷልና ፥ በርሷ ፡ ላይ ፡ ስበክ ።

3 ፤ ዮናስ ፡ ግን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ወደ ፡ ተርሴስ ፡ ይኰበልል ፡ ዘንድ ፡ ተነሣ ፤ ወደ ፡ ኢዮጴም ፡ ወረደ ፥ ወደ ፡
ተርሴስም ፡ የምታልፍ ፡ መርከብ ፡ አገኘ ፤ ከእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ኰብሎ ፡ ከነርሱ ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ ተርሴስ ፡ ይኼድ ፡
ዘንድ ፡ ዋጋ ፡ ሰጥቶ ፡ ወደ ፡ ርሷ ፡ ገባ ።

4 ፤ እግዚአብሔርም ፡ በባሕሩ ፡ ላይ ፡ ታላቅ ፡ ነፋስን ፡ አመጣ ፥ በባሕርም ፡ ላይ ፡ ታላቅ ፡ ማዕበል ፡ ኾነ ፥ መርከቢቱም ፡
ልትሰበር ፡ ቀረበች ።

5 ፤ መርከበኛዎቹም ፡ ፈሩ ፥ እያንዳንዱም ፡ ወደ ፡ አምላኩ ፡ ጮኸ ፤ መርከቢቱም ፡ እንድትቀልላቸው ፡ በውስጧ ፡
የነበረውን ፡ ዕቃ ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ጣሉት ፤ ዮናስ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ መርከቡ ፡ ውስጠኛው ፡ ክፍል ፡ ወርዶ ፡ ነበር ፥ በከባድ ፡
እንቅልፍም ፡ ተኝቶ ፡ ነበር ።

6 ፤ የመርከቡም ፡ አለቃ ፡ ወደ ፡ ርሱ ፡ ቀርቦ ፦ ምነው ፡ ተኝተኻል ፧ እንዳንጠፋ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያስበን ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡
ተነሥተኽ ፡ አምላክኽን ፡ ጥራ ፡ አለው ።

7 ፤ ርስ ፡ በርሳቸውም ፦ ይህ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ በማን ፡ ምክንያት ፡ እንዳገኘን ፡ እናውቅ ፡ ዘንድ ፡ ኑ ፥ ዕጣ ፡ እንጣጣል ፡
ተባባሉ ። ዕጣም ፡ ተጣጣሉ ፥ ዕጣውም ፡ በዮናስ ፡ ላይ ፡ ወደቀ ።

8 ፤ የዚያን ፡ ጊዜም ፦ ይህ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ በማን ፡ ምክንያት ፡ እንዳገኘን ፡ እባክኽ ፡ ንገረን ፤ ሥራኽ ፡ ምንድር ፡
ነው ፧ ከወዴትስ ፡ መጣኽ ፧ አገርኽስ ፡ ወዴት ፡ ነው ፧ ወይስ ፡ ከማን ፡ ወገን ፡ ነኽ ፧ አሉት ።

9 ፤ ርሱም ፦ እኔ ፡ ዕብራዊ ፡ ነኝ ፤ ባሕሩንና ፡ የብሱን ፡ የፈጠረውን ፡ የሰማይን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡
አመልካለኍ ፡ አላቸው ።

10 ፤ እነዚያም ፡ ሰዎች ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እንደ ፡ ኰበለለ ፡ ርሱ ፡ ስለ ፡ ነገራቸው ፡ ዐውቀዋልና ፥ እጅግ ፡
ፈርተው ፦ ይህ ፡ ያደረግኸው ፡ ምንድር ፡ ነው ፧ አሉት ።

11 ፤ ባሕሩንም ፡ ሞገዱ ፡ አጥብቆ ፡ ያናውጠው ፡ ነበርና ፦ ባሕሩ ፡ ከእኛ ፡ ዘንድ ፡ ጸጥ ፡ እንዲል ፡ ምን ፡
እናድርግብኽ ፧ አሉት ።

12 ፤ ርሱም ፦ ይህ ፡ ታላቅ ፡ ማዕበል ፡ በእኔ ፡ ምክንያት ፡ እንዳገኛችኍ ፡ ዐውቃለኍና ፡ አንሥታችኍ ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡
ጣሉኝ ፥ ባሕሩም ፡ ጸጥ ፡ ይልላችኋል ፡ አላቸው ።

13 ፤ ሰዎቹ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ምድሩ ፡ ሊመለሱ ፡ አጥብቀው ፡ ቀዘፉ ፤ ዳሩ ፡ ግን ፡ ባሕሩ ፡ እጅግ ፡ አብዝቶ ፡ ይናወጥባቸው ፡
ነበርና ፥ አልቻሉም ።

14 ፤ ስለዚህ ፥ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኸው ፦ አቤቱ ፥ እንደ ፡ ወደድኽ ፡
አድርገኻልና ፥ እንለምንኻለን ፤ አቤቱ ፥ ስለዚህ ፡ ሰው ፡ ነፍስ ፡ እንዳንጠፋ ፡ ንጹሕም ፡ ደም ፡ በእኛ ፡ ላይ ፡
እንዳታደርግ ፡ እንለምንኻለን ፡ አሉ ።

15 ፤ ዮናስንም ፡ ወስደው ፡ ወደ ፡ ባሕሩ ፡ ጣሉት ፤ ባሕሩም ፡ ከመናወጡ ፡ ጸጥ ፡ አለ ።

16 ፤ ሰዎችም ፡ እግዚአብሔርን ፡ እጅግ ፡ ፈሩ ፥ ለእግዚአብሔርም ፡ መሥዋዕትን ፡ አቀረቡ ፥ ስእለትንም ፡ ተሳሉ ።

ትንቢተ ፡ ዮናስ ፥ ምዕራፍ ፡ 2 ።

ምዕራፍ ፡ 2 ።

1 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ዮናስን ፡ የሚውጥ ፡ ታላቅ ፡ ዓሣ ፡ አሰናዳ ፤ ዮናስም ፡ ሦስት ፡ ቀንና ፡ ሦስት ፡ ሌሊት ፡ በዓሣው ፡ ሆድ ፡ ውስጥ ፡ ነበረ ።

2 ፤ ዮናስም ፡ በዓሣው ፡ ሆድ ፡ ውስጥ ፡ ኾኖ ፡ ወደ ፡ አምላኩ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸለየ ፥ እንዲህም ፡ አለ ፦

3 ፤ በመከራዬ ፡ ሳለኹ ፡ ወደ ፡ አምላኬ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኽኹ ፥ ርሱም ፡ ሰማኝ ፤ በሲኦልም ፡ ሆድ ፡ ውስጥ ፡ ኾኜ ፡ ጮኽኹ ፥ ቃሌንም ፡ አዳመጥኽ ።

4 ፤ ወደ ፡ ጥልቁ ፡ ወደ ፡ ባሕሩ ፡ ውስጥ ፡ ጣልኸኝ ፥ ፈሳሾችም ፡ በዙሪያዬ ፡ ነበሩ ፤ ማዕበልኽና ፡ ሞገድኽ ፡ ዅሉ ፡ በላዬ ፡ ዐለፉ ።

5 ፤ እኔም ፦ ከዐይንኽ ፡ ፊት ፡ ተጣልኹ ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ወደ ፡ ቅዱስ ፡ መቅደስኽ ፡ ደግሞ ፡ እመለከታለኹ ፡ አልኹ ።

6 ፤ ውሃዎችም ፡ እስከ ፡ ነፍሴ ፡ ድረስ ፡ ከበቡኝ ፤ ጥልቁ ፡ ባሕር ፡ በዙሪያዬ ፡ ነበረ ፤ የባሕሩ ፡ ሣር ፡ በራሴ ፡ ተጠምጥሞ ፡ ነበር ።

7 ፤ ወደተራራዎች ፡ መሠረት ፡ ወረድኹ ፤ በምድርና ፡ በመወርወሪያዎቿ ፡ ለዘለዓለም ፡ ተዘጋኹ ፤ አንተ ፡ ግን ፥ አቤቱ ፡ አምላኬ ፥ ሕይወቴን ፡ ከጕድጓዱ ፡ አወጣኽ ።

8 ፤ ነፍሴ ፡ በዛለችብኝ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ዐሰብኹት ፤ ጸሎቴም ፡ ወዳንተ ፡ ወደ ፡ ቅዱስ ፡ መቅደስኽ ፡ ገባች ።

9 ፤ ከንቱነትንና ፡ ሐሰትን ፡ የሚጠብቁ ፡ ምሕረታቸውን ፡ ትተዋል ።

10 ፤ እኔ ፡ ግን ፡ በምስጋና ፡ ቃል ፡ እሠዋልኻለኹ ፤ የተሳልኹትንም ፡ እከፍላለኹ ። ደኅንነት ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ነው ።

11 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ዓሣውን ፡ አዘዘው ፥ ርሱም ፡ ዮናስን ፡ በየብስ ፡ ላይ ፡ ተፋው ።

ትንቢተ ፡ ዮናስ ፥ ምዕራፍ ፡ 3 ።

ምዕራፍ ፡ 3 ።

1 ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ኹለተኛ ፡ ወደ ፡ ዮናስ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፦

2 ፤ ተነሥተኽ ፡ ወደዚያች ፡ ወደ ፡ ታላቂቱ ፡ ከተማ ፡ ወደ ፡ ነነዌ ፡ ኺድ ፥ የምነግርኽንም ፡ ስብከት ፡ ስበክላት ፡ አለው ።

3 ፤ ዮናስም ፡ ተነሥቶ ፡ እንደእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ ነነዌ ፡ ኼደ ፤ ነነዌም ፡ የሦስት ፡ ቀን ፡ መንገድ ፡ ያኽል ፡ እጅግ ፡ ታላቅ ፡ ከተማ ፡ ነበረች ።

4 ፤ ዮናስም ፡ የአንድ ፡ ቀን ፡ መንገድ ፡ ያኽል ፡ ወደ ፡ ከተማዪቱ ፡ ውስጥ ፡ ሊገባ ፡ ዠመረ ፤ ጮኾም ፦ በሦስት ፡ ቀን ፡ ውስጥ ፡ ነነዌ ፡ ትገለበጣለች ፡ አለ ።

5 ፤ የነነዌም ፡ ሰዎች ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመኑ ፤ ለጾም ፡ ዐዋጅ ፡ ነገሩ ፥ ከታላቁም ፡ ዠምሮ ፡ እስከ ፡ ታናሹ ፡ ድረስ ፡ ማቅ ፡ ለበሱ ።

6 ፤ ወሬውም ፡ ወደነነዌ ፡ ንጉሥ ፡ ደረሰ ፤ ርሱም ፡ ከዙፋኑ ፡ ተነሥቶ ፡ መጐናጸፊያውን ፡ አወለቀ ፡ ማቅም ፡ ለበሰ ፥ በዐመድም ፡ ላይ ፡ ተቀመጠ ።

7 ፤ ዐዋጅም ፡ አስነገረ ፥ በነነዌም ፡ ውስጥ ፡ የንጉሡንና ፡ የመኳንንቱን ፡ ትእዛዝ ፡ አሳወጀ ፥ እንዲህም ፡ አለ ፦ ሰዎችና ፡ እንስሳዎች ፡ ላሞችና ፡ በጎች ፡ አንዳችን ፡ አይቅመሱ ፤ አይሰማሩም ፡ ውሃንም ፡ አይጠጡ ፤

8 ፤ ሰዎችና ፡ እንስሳዎችም ፡ በማቅ ፡ ይከደኑ ፥ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ በብርቱ ፡ ይጮኹ ፤ ሰዎችም ፡ ዅሉ ፡ ከክፉ ፡ መንገዳቸውና ፡ በእጃቸው ፡ ካለው ፡ ግፍ ፡ ይመለሱ ።

9 ፤ እኛ ፡ እንዳንጠፋ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተመልሶ ፡ ይጸጸት ፡ እንደ ፡ ኾነ ፥ ከጽኑ ፡ ቍጣውም ፡ ይመለስ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ ማን ፡ ያውቃል ፨

10 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ከክፉ ፡ መንገዳቸው ፡ እንደተመለሱ ፡ ሥራቸውን ፡ አየ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ያደርግባቸው ፡
ዘንድ ፡ በተናገረው ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ተጸጽቶ ፡ አላደረገውም ።

ትንቢተ ፡ ዮናስ ፥ ምዕራፍ ፡ 4 ።

ምዕራፍ ፡ 4 ።

1 ፤ ይህም ፡ ዮናስን ፡ ከቶ ፡ ደስ ፡ አላሠኘውም ፥ ርሱም ፡ ተቈጣ ።

2 ፤ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ጸለየና ፦ አቤቱ ፥ እለምንኻለኹ ፤ በአገሬ ፡ ሳለኹ ፡ የተናገርኹት ፡ ይህ ፡
አልነበረምን ፤ አንተ ፡ ቸርና ፡ ይቅር ፡ ባይ ፥ ታጋሽም ፥ ምሕረትኽም ፡ የበዛ ፥ ከክፉው ፡ ነገርም ፡ የተነሣ ፡ የምትጸጸት ፡
አምላክ ፡ እንደ ፡ ኾንኽ ፡ ዐውቄ ፡ ነበርና ፥ ስለዚህ ፡ ወደ ፡ ተርሴስ ፡ ለመኰብለል ፡ ፈጥኜ ፡ ነበር ።

3 ፤ አኹንም ፥ አቤቱ ፥ ከሕይወት ፡ ሞት ፡ ይሻለኛልና ፥ እባክኽ ፥ ነፍሴን ፡ ከእኔ ፡ ውሰድ ፡ አለው ።

4 ፤ እግዚአብሔርም ፦ በእውኑ ፡ ትቈጣ ፡ ዘንድ ፡ ይገ፟ባ፟ኻልን ፤ አለ ።

5 ፤ ዮናስም ፡ ከከተማዪቱ ፡ ወጣ ፥ ከከተማዪቱም ፡ በስተምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ተቀመጠ ፤ ከተማዪቱንም ፡ የሚያገኛትን ፡
እስኪያይ ፡ ድረስ ፡ በዚያ ፡ ለራሱ ፡ ዳስ ፡ ሠርቶ ፡ ከጥላው ፡ በታች ፡ ተቀመጠ ።

6 ፤ እግዚአብሔር ፡ አምላክም ፡ ቅል ፡ አዘጋጀ ፥ ከጭንቀቱም ፡ ታድነው ፡ ዘንድ ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ጥላ ፡ እንድትኾን ፡
በዮናስ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረጋት ፤ ዮናስም ፡ ስለ ፡ ቅሊቱ ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ አለው ።

7 ፤ በነጋው ፡ ግን ፡ ወገግ ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ትልን ፡ አዘጋጀ ፥ ርሷም ፡ ቅሊቱን ፡ እስክትደርቅ ፡ ድረስ ፡
መታቻት ።

8 ፤ ፀሓይም ፡ በወጣች ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ትኵስ ፡ የምሥራቅ ፡ ነፋስ ፡ አዘጋጀ ፡ ዮናስ ፡ እስኪዝል ፡ ድረስም ፡ ፀሓይ ፡
ራሱን ፡ መታው ፤ ለራሱም ፡ ሞትን ፡ ፈለገና ፦ ከሕይወት ፡ ሞት ፡ ይሻለኛል ፡ አለ ።

9 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ዮናስን ፦ በእውኑ ፡ ስለዚች ፡ ቅል ፡ ትቈጣ ፡ ዘንድ ፡ ይገ፟ባ፟ኻልን ፤ አለው ። ርሱም ፦ እስከ ፡
ሞት ፡ ድረስ ፡ እቈጣ ፡ ዘንድ ፡ ይገ፟ባ፟ኛል ፡ አለ ።

10 ፤ እግዚአብሔርም ፦ አንተ ፡ ትበቅል ፡ ዘንድ ፡ ላልደከምኽባት ፡ ላላሳደግኻትም ፥ ባንድ ፡ ሌሊት ፡ ለበቀለች ፥ ባንድ ፡
ሌሊትም ፡ ለደረቀችው ፡ ቅል ፡ አዝነኻል ።

11 ፤ እኔስ ፡ ቀኛቸውንና ፡ ግራቸውን ፡ የማይለዩ ፡ ከመቶ ፡ ኻያ ፡ ሺሕ ፡ የሚበልጡ ፡ ሰዎችና ፡ ብዙ ፡ እንስሳዎች ፡
ላሉባት ፡ ለታላቂቱ ፡ ከተማ ፡ ለነነዌ ፡ አላዝንምን ፤ አለው ፨

# ትንቢተ ፡ ሚክያስ ።

(ክለሳ.1.20020507)

ትንቢተ ፡ ሚክያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 1 ።

ምዕራፍ ፡ 1 ።

1 ፤ በይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ በኢዮአታምና ፡ በአካዝ ፡ በሕዝቅያስም ፡ ዘመን ፡ ወደ ፡ ሞሬታዊው ፡ ወደ ፡ ሚክያስ ፡
የመጣው ፥ ስለ ፡ ሰማርያና ፡ ስለ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ያየው ፥ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ፦

2 ፤ እናንተ ፡ አሕዛብ ፡ ኹሉ ፥ ስሙ ፤ ምድርም ፡ መላዋም ፡ ታድምጥ ፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፥ ርሱም ፡ በቅዱስ ፡
መቅደሱ ፡ የኾነ ፡ ጌታ ፥ ይመስክርባችኹ ።

3 ፤ እንሆ ፥ እግዚአብሔር ፡ ከስፍራው ፡ ይወጣል ፥ ወርዶም ፡ በምድር ፡ ከፍታዎች ፡ ላይ ፡ ይረግጣል ።

4 ፤ ተራራዎችም ፡ በእሳት ፡ ፊት ፡ እንዳለ ፡ ሠም ፥ በገደልም ፡ ወርዶ ፡ እንደሚፈስ ፡ ውሃ ፥ በበታቹ ፡
ይቀልጣሉ ፥ ሸለቆዎችም ፡ ይሰነጠቃሉ ።

5 ፤ ይህ ፡ ኹሉ ፡ ስለ ያዕቆብ ፡ በደልና ፡ ስለእስራኤል ፡ ቤት ፡ ኀጢአት ፡ ነው ። የያዕቆብም ፡ በደል ፡ ምንድር ፡
ነው ፧ ሰማርያ ፡ አይደለችምን ፧ የይሁዳስ ፡ የኰረብታው ፡ መስገጃ ፡ ምንድር ፡ ነው ፧ ኢየሩሳሌም ፡ አይደለችምን ፧

6 ፤ ስለዚህ ፥ ሰማርያን ፡ በሜዳ ፡ እንደሚገኝ ፡ የድንጋይ ፡ ክምር ፥ ወይን ፡ እንደሚተከልበትም ፡ ስፍራ ፡
አደርጋታለኹ ፤ ድንጋዮቿንም ፡ ወደ ፡ ሸለቆ ፡ እወረውራለኹ ፥ መሠረቶቿንም ፡ እገልጣለኹ ።

7 ፤ የተቀረጹትም ፡ ምስሎቿ ፡ ይደቀቃሉ ፥ በግልሙትና ፡ ያገኘችው ፡ ዋጋ ፡ ኹሉ ፡ በእሳት ፡ ይቃጠላል ፥ ጣዖታቷንም ፡
ኹሉ ፡ አጠፋለኹ ፤ በግልሙትና ፡ ዋጋ ፡ ሰበሰበቻቸው ፥ ወደ ፡ ግልሙትናም ፡ ዋጋ ፡ ይመለሳሉና ።

8 ፤ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ዋይ ፡ ብላ ፡ ታለቅሳለች ፥ ባዶ ፡ እግሯንና ፡ ዕራቍቷን ፡ ኾና ፡ ትኼዳለች ፤ እንደ ፡ ቀበሮ ፡
ታለቅሳለች ፥ እንደ ፡ ሰጐንም ፡ ዋይ ፡ ትላለች ፤

9 ፤ ቍስሏ ፡ የማይፈወስ ፡ ነውና ፤ እስከ ፡ ይሁዳም ፡ ደርሷልና ፥ ወደሕዝቤም ፡ በር ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ቀርቧልና ።

10 ፤ በጌት ፡ ላይ ፡ አታውሩ ፤ በአኮ ፡ ላይ ፡ እንባን ፡ አታድርጉ ፤ በቤትዓፍራ ፡ በትቢያ ፡ ላይ ፡ ተንከባለሉ ።

11 ፤ በሻፊር ፡ የምትቀመጪ ፡ ሆይ ፥ በዕራቍትነትሽና ፡ በዕፍረት ፡ ዕለፊ ፤ በጸዓናን ፡ የምትቀመጠው ፡
አልወጣችም ፤ የቤትኤጼል ፡ ልቅሶ ፡ ከእናንተ ፡ ዘንድ ፡ መኖሪያውን ፡ ይወስዳል ።

12 ፤ ክፉ ፡ ነገር ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ እስከኢየሩሳሌም ፡ በር ፡ ድረስ ፡ ወርዷልና ፥ በማሮት ፡ የምትቀመጠው ፡
በጎነትን ፡ ትጠባበቃለች ።

13 ፤ በለኪሶ ፡ የምትቀመጪ ፡ ሆይ ፥ ሠረገላውን ፡ ለፈረስ ፡ እሰሪ ፤ ርሷ ፡ ለጽዮን ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ የኀጢአት ፡
መዠመሪያ ፡ ነበረች ፤ የእስራኤል ፡ በደል ፡ ባንቺ ፡ ዘንድ ፡ ተገኝቷልና ።

14 ፤ ስለዚህ ፥ ትሎት ፡ ለሞሬሼትጌት ፡ ትሰጪያለሽ ፤ የአክዚብ ፡ ቤቶች ፡ ለእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ አታላይ ፡ ይኾናሉ ።

15 ፤ በመሪሳ ፡ የምትቀመጪ ፡ ሆይ ፥ ወራሽ ፡ አመጣብሻለኹ ፤ የእስራኤል ፡ ክብር ፡ ወደ ፡ ዓዶላም ፡ ይመጣል ።

16 ፤ ተማርከው ፡ ከአንቺ ፡ ዘንድ ፡ ወጥተዋልና ፥ ስለተድላሽ ፡ ልጆች ፡ ራስሽን ፡ ንጪ ፥ ጠጕርሽንም ፡
ተቈረጪ ፤ ቡሓነትሽንም ፡ እንደ ፡ ንስር ፡ አስፊ ።

ትንቢተ ፡ ሚክያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 2 ።

ምዕራፍ ፡ 2 ።

1 ፤ በመኝታቸው ፡ ላይ ፡ በደልን ፡ ለሚያስቡ ፡ ክፋትንም ፡ ለሚያደርጉ ፡ ወዮላቸው! ኀይል ፡ በእጃቸው ፡ ነውና ፥ ሲነጋ ፡
ይፈጽሙታል ።

2 ፤ በዕርሻው ፡ ላይ ፡ ይመኛሉ ፥ በግዴታም ፡ ይይዙታል ፤ በቤቶችም ፡ ላይ ፡ ይመኛሉ ፥ ይወስዷቸውማል ፤ ሰውንና ፡
ቤቱን ፥ ሰውንና ፡ ርስቱንም ፡ ይነጥቃሉ ።

3 ፤ ስለዚህ ፥ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ እንሆ ፥ በዚህ ፡ ወገን ፡ ላይ ፡ በክፉ ፡ ዐስባለኹ ፥ ከዚያም ፡
ዐንገታችኹን ፡ አታነሡም ፤ ዘመኑም ፡ ክፉ ፡ ነውና ፥ ቀጥ ፡ ብላችኹ ፡ አትኼዱም ።

4 ፤ በዚያ ፡ ቀን ፡ በምሳሌ ፡ ይመስሉባች኿ል ፥ በጽኑ ፡ ልቅሶም ፡ ያለቅሱላች኿ል ፤ እነርሱም ፦ ፈጽመን ፡
ጠፍተናል ፤ የሕዝቤን ፡ ዕድል ፡ ፈንታ ፡ ይሰፍራል ፥ ርሱንም ፡ የሚከለክል ፡ የለም ፤ ዕርሻችንን ፡ ለዐመፀኛዎች ፡
ይከፍላል ፡ ይላሉ ።

5 ፤ ስለዚህ ፥ በእግዚአብሔር ፡ ጉባኤ ፡ መካከል ፡ በዕጣ ፡ ገመድ ፡ የሚጥል ፡ አይኖርኽም ።

6 ፤ ትንቢት ፡ አትናገሩ ፡ ብለው ፡ ይናገራሉ ፤ በእነዚህ ፡ ላይ ፡ ትንቢት ፡ አይናገሩም ፥ ስድብም ፡ አይርቅም ።

7 ፤ የያዕቆብ ፡ ቤት ፡ የተባልኽ ፡ ሆይ ፥ በእውኑ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ የማይታገሥ ፡ ነውን ፧ ወይስ ፡ ሥራው ፡
እንደዚኽ ፡ ናትን ፧ ቃሌስ ፡ በቅን ፡ ለሚኼድ ፡ በጎነት ፡ አያደርግምን ፧

8 ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ከቅርብ ፡ ጊዜ ፡ ዠምሮ ፡ ሕዝቤ ፡ እንደ ፡ ጠላት ፡ ኾኖ ፡ ተነሥቷል ፤ ቀሚስንና ፡ መጐናጸፊያን ፡
ገፈፉችኹ ፤ ሳይፈሩም ፤ የሚያልፉትን ፡ ከሰልፍ ፡ እንደሚመለሱ ፡ አደረጋች኿ቸው ።

9 ፤ የሕዝቤንም ፡ ሴቶች ፡ ከተሸለሙ ፡ ቤቶቻቸው ፡ አሳደዳች኿ቸው ፤ ከሕፃናታቸውም ፡ ክብሬን ፡ ለዘለዓለም ፡
ወሰዳችኹ ።

10 ፤ በዚህ ፡ ዕረፍት ፡ የላችኹምና ፡ ተነሥታችኹ ፡ ኺዱ ፤ በርኵሰት ፡ ምክንያት ፡ ክፉ ፡ ጥፋት ፡ ታጠፋች኿ለች ።

11 ፤ ነፋስንም ፡ ተከትሎ ፦ ስለወይን ፡ ጠጅና ፡ ስለ ፡ ስካር ፡ ትንቢት ፡ እናገርልኻለኹ ፡ ብሎ ፡ ሐሰትን ፡ የሚናገር ፡
ሰው ፡ ቢኖር ፡ ርሱ ፡ ለዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ነቢይ ፡ ይኾናል ።

12 ፤ ያዕቆብ ፡ ሆይ ፥ ዅለንተናኽን ፡ ፈጽሞ ፡ እሰበስባለኹ ፥ የእስራኤልንም ፡ ቅሬታ ፡ ፈጽሞ ፡ አከማቻለኹ ፤ እንደ ፡
ባሶራ ፡ በጎችና ፡ እንደ ፡ መንጋ ፡ በማሰማሪያቸው ፡ ውስጥ ፡ በአንድነት ፡ አኖራቸዋለኹ ፤ ከሰው ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡
ድምፃቸውን ፡ ያሰማሉ ።

13 ፤ ሰባሪው ፡ በፊታቸው ፡ ወጥቷል ፤ እነርሱም ፡ ሰብረው ፡ ወደ ፡ በሩ ፡ አልፈዋል ፥ በርሱም ፡ በኩል ፡
ወጥተዋል ፤ ንጉሣቸውም ፡ በፊታቸው ፡ ዐልፏል ፥ እግዚአብሔርም ፡ በራሳቸው ፡ ላይ ፡ ነው ።

___________________ትንቢተ ፡ ሚክያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 3 ። ___________________

ምዕራፍ ፡ 3 ።

1 ፤ እንዲህም ፡ አልኹ ። የያዕቆብ ፡ አለቃዎችና ፡ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ገዢዎች ፡ ሆይ ፥ እባካችኹ ፡ ስሙኝ ፤ ፍርድን ፡
ታውቁ ፡ ዘንድ ፡ አይገባችኹምን ፧

2 ፤ መልካሙን ፡ ጠልታች኿ል ፥ ክፉውንም ፡ ወዳች኿ል ፤ ቍርበታቸውን ፡ ገፋች኿ቸዋል ፥ ሥጋቸውንም ፡
ከዐጥንታቸው ፡ ለያይታች኿ል ፤

3 ፤ የሕዝቤን ፡ ሥጋ ፡ በልታች኿ል ፥ ቍርበታቸውንም ፡ ገፋች኿ቸዋል ፥ ዐጥንታቸውንም ፡ ሰብራች኿ል ፤ ለአፍላል ፡
እንደሚኾን ፡ ሥጋ ፡ ለድስትም ፡ እንደሚኾን ፡ ሙዳ ፡ ቈራረጣች኿ቸው ።

4 ፤ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይጮኻሉ ፥ ርሱም ፡ አይሰማቸውም ፤ ሥራቸውንም ፡ ክፉ ፡
አድርገዋልና ፥ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ ፊቱን ፡ ከነርሱ ፡ ይሰውራል ።

5 ፤ እግዚአብሔር ፡ ሕዝቤን ፡ ስለሚያስቱ ፡ ነቢያት ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፤ በጥርሳቸው ፡ ሲነክሱ ፡ በሰላም ፡
ይሰብካሉ ፤ በአፋቸው ፡ ግን ፡ አንዳች ፡ በማይሰጥ ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ ሰልፍን ፡ ያስቡበታል ።

6 ፤ ስለዚህ ፥ ሌሊት ፡ ይኾንባች኿ል ፡ እንጂ ፡ ራእይ ፡ አይኾንላችኹም ፤ ጨለማም ፡ ይኾንባች኿ል ፡ እንጂ ፡
አታሟርቱም ፤ ፀሓይም ፡ በነቢያት ፡ ላይ ፡ ትገባለች ፥ ቀኑም ፡ ይጠቍርባቸዋል ።

7 ፤ ከእግዚአብሔርም ፡ ዘንድ ፡ መልስ ፡ የለምና ፡ ባለራእዮቹ ፡ ያፍራሉ ፥ ሟርተኛዎችም ፡ ይዋረዳሉ ፤ ዅሉም ፡

ከንፈራቸውን ፡ ይሸፍናሉ ።

8 ፤ እኔ ፡ ግን ፡ በደሉን ፡ ለያዕቆብ ፥ ኀጢአቱንም ፡ ለእስራኤል ፡ እነግር ፡ ዘንድ ፡ በእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ ኀይልንና ፡
ፍርድን ፡ ብርታትንም ፡ ተሞልቻለኹ ።

9 ፤ ፍርድን ፡ የምትጠሉ ፡ ቅን ፡ ነገርንም ፡ ኹሉ ፡ የምታጣምሙ ፡ እናንተ ፡ የያዕቆብ ፡ ቤት ፡ አለቃዎችና ፡ የእስራኤል ፡
ቤት ፡ ገዢዎች ፡ ሆይ ፥ እባካችኹ ፡ ይህን ፡ ስሙ ።

10 ፤ ጽዮንን ፡ በደም ፥ ኢየሩሳሌምንም ፡ በኀጢአት ፡ ይሠራሉ ።

11 ፤ አለቃዎቿ ፡ በጉቦ ፡ ይፈርዳሉ ፥ ካህናቷም ፡ በዋጋ ፡ ያስተምራሉ ፥ ነቢያቷም ፡ በገንዘብ ፡ ያሟርታሉ ፤ ከዚህም ፡
ጋራ ። እግዚአብሔር ፡ በመካከላችን ፡ አይደለምን ፧ ክፉ ፡ ነገር ፡ ምንም ፡ አይመጣብንም ፡ እያሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ይታመናሉ ።

12 ፤ ስለዚህ ፥ በእናንተ ፡ ምክንያት ፡ ጽዮን ፡ እንደ ፡ ዕርሻ ፡ ትታረሳለች ፥ ኢየሩሳሌምም ፡ የድንጋይ ፡ ክምር ፡
ትኾናለች ፥ የቤቱም ፡ ተራራ ፡ እንደ ፡ ዱር ፡ ከፍታ ፡ ይኾናል ።

____________________ትንቢተ ፡ ሚክያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 4 ። ____________________

ምዕራፍ ፡ 4 ።

1 ፤ በመጨረሻውም ፡ ዘመን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ተራራ ፡ በተራራዎች ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ጸንቶ ፡
ይቆማል ፥ ከኮረብታዎችም ፡ በላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ፤ አሕዛብም ፡ ወደ ፡ ርሱ ፡ ይጐርፋሉ ።

2 ፤ ከጽዮን ፡ ሕግ ፥ ከኢየሩሳሌምም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ይወጣልና ፥ ብዙዎች ፡ አሕዛብ ፡
ኼደው ፦ ኑ ፥ ወደእግዚአብሔር ፡ ተራራ ፥ ወደያዕቆብ ፡ አምላክ ፡ ቤት ፡ እንውጣ ፤ ርሱም ፡ መንገዱን ፡
ያስተምረናል ፥ በፍለጋውም ፡ እንኼዳለን ፡ ይላሉ ።

3 ፤ በብዙዎችም ፡ አሕዛብ ፡ መካከል ፡ ይፈርዳል ፥ በሩቅም ፡ ባሉ ፡ በብርቱዎች ፡ አሕዛብ ፡ ላይ ፡
ይበይናል ፤ ሰይፋቸውንም ፡ ማረሻ ፥ ጦራቸውንም ፡ ማጭድ ፡ ለማድረግ ፡ ይቀጠቅጣሉ ፤ ሕዝብም ፡ በሕዝብ ፡ ላይ ፡
ሰይፍ ፡ አያነሣም ፡ ከእንግዲህም ፡ ወዲህ ፡ ሰልፍ ፡ አይማሩም ።

4 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔር ፡ አፍም ፡ ተናግሯልና ፥ ሰው ፡ እያንዳንዱ ፡ ከወይኑና ፡ ከበለሱ ፡ በታች ፡
ይቀመጣል ፥ የሚያስፈራውም ፡ የለም ።

5 ፤ ሕዝብም ፡ ኹሉ ፡ እያንዳንዱ ፡ በያምላኩ ፡ ስም ፡ ይኼዳል ፥ እኛም ፡ በአምላካችን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡
ለዘለዓለም ፡ እንኼዳለን ።

6 ፤ በዚያ ፡ ቀን ፡ ዐንካሳዪቱን ፡ እሰበስባለኹ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፥ የባከነችውንና ፡ ያስጨነቅኋትንም ፡ አከማቻለኹ ፤

7 ፤ ዐንካሳዪቱንም ፡ ለቅሬታ ፥ ወደ ፡ ሩቅም ፡ የተጣለችውን ፡ ለብርቱ ፡ ሕዝብ ፡ አደርጋታለኹ ፤ ከዚያም ፡ ወዲያ ፡
እስከ ፡ ዘለዓለም ፡ ድረስ ፡ እግዚአብሔር ፡ በጽዮን ፡ ተራራ ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ይነግሣል ።

8 ፤ አንተም ፡ የመንጋ ፡ ግንብ ፡ ሆይ ፥ የጽዮን ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ዐምባ ፥ ወዳንተ ፡ ትመጣለች ፤ የቀደመችው ፡
ግዛት ፥ የኢየሩሳሌም ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ መንግሥት ፡ ትደርሳለች ።

9 ፤ አኹንስ ፡ ለምን ፡ ትጮኺያለሽ ፧ እንደምትወልድ ፡ ሴት ፡ ምጥ ፡ የደረሰብሽ ፥ ንጉሥ ፡ ስለሌለሽ ፡ ነውን ፧ ወይስ ፡
መካሪ ፡ ስለ ፡ ጠፋብሽ ፡ ነውን ፧

10 ፤ የጽዮን ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ እንደምትወልድ ፡ ሴት ፡ አምጠሽ ፡ ውለጂ ፤ አኹን ፡ ከከተማ ፡ ትወጫለሽና ፥ በሜዳም ፡
ትቀመጫለሽ ፥ ወደ ፡ ባቢሎንም ፡ ትደርሻለሽ ፤ በዚያም ፡ ያድንሻል ፥ በዚያም ፡ እግዚአብሔር ፡ ከጠላቶችሽ ፡ እጅ ፡
ይቤዠሻል ።

11 ፤ አኹንም ፦ ርኩስ ፡ ትኹን ፥ ዐይናችንም ፡ በጽዮን ፡ ላይ ፡ ይይ ፡ የሚሉ ፡ ብዙ ፡ አሕዛብ ፡ ባንቺ ፡ ላይ ፡
ተሰብስበዋል ።

12 ፤ ነገር ፡ ግን ፥ የእግዚአብሔርን ፡ ዐሳብ ፡ አያውቁም ፥ ምክሩንም ፡ አያስተውሉም ፤ እንደ ፡ ነዶ ፡ ወደ ፡ ዐውድማ ፡

አከማችቷቸዋልና ።

13 ፤ የጽዮን ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ ቀንድሽን ፡ ብረት ፥ ጥፍርሽንም ፡ ናስ ፡ አደርጋለኹና ፡ ተነሺ ፥ አኺጂ ፤ ብዙ ፡ አሕዛብንም ፡ ታደቂያለሽ ፤ ትርፋቸውንም ፡ ለእግዚአብሔር ፥ ሀብታቸውንም ፡ ለምድር ፡ ኹሉ ፡ ጌታ ፡ ትቀድሻለሽ ።

ትንቢተ ፡ ሚክያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 5 ።

ምዕራፍ ፡ 5 ።

1 ፤ የጭፍራዎች ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ ጭፍራዎችሽን ፡ አኹን ፡ ሰብስቢ ፤ ከቦ ፡ አስጨንቆናል ፤ የእስራኤልን ፡ ፈራጅ ፡ ጕንጩን ፡ በበትር ፡ ይመታሉ ።

2 ፤ አንቺም ፡ ቤተ ፡ ልሔም ፡ ኤፍራታ ፡ ሆይ ፥ አንቺ ፡ በይሁዳ ፡ አእላፋት ፡ መካከል ፡ ትኾኚ ፡ ዘንድ ፡ ታናሽ ፡ ነሽ ፤ ከአንቺ ፡ ግን ፡ አወጣጡ ፡ ከቀድሞ ፡ ዠምሮ ፡ ከዘለዓለም ፡ የኾነ ፥ በእስራኤልም ፡ ላይ ፡ ገዢ ፡ የሚኾን ፡ ይወጣልኛል ።

3 ፤ ስለዚህ ፥ ወላጂቱ ፡ እስከምትወልድበት ፡ ጊዜ ፡ ድረስ ፡ አሳልፎ ፡ ይሰጣቸዋል ፤ የቀሩትም ፡ ወንድሞቹ ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ልጆች ፡ ይመለሳሉ ።

4 ፤ ርሱም ፡ ይቆማል ፥ በእግዚአብሔርም ፡ ኀይል ፡ በአምላኩ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ግርማ ፡ መንጋውን ፡ ይጠብቃል ፤ እነርሱም ፡ ይኖራሉ ፤ ርሱ ፡ አኹን ፡ እስከምድር ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ ታላቅ ፡ ይኾናልና ።

5 ፤ ይህም ፡ ሰላም ፡ ይኾናል ፤ አሶራዊውም ፡ ወደ ፡ አገራችን ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፥ ምድራችንንም ፡ በረገጠ ፡ ጊዜ ፡ ሰባት ፡ እረኛዎችና ፡ ስምንት ፡ አለቃዎች ፡ እናስነሣበታለን ።

6 ፤ የአሶርንም ፡ አገር ፡ በሰይፍ ፥ የናምሩድንም ፡ አገር ፡ በመግቢያው ፡ ውስጥ ፡ ያፈርሳሉ ፤ አሶራዊውም ፡ ወደ ፡ አገራችን ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፥ ዳርቻዎቻችንንም ፡ በረገጠ ፡ ጊዜ ፡ ርሱ ፡ ይታደገናል ።

7 ፤ የያዕቆብም ፡ ቅሬታ ፡ በብዙ ፡ አሕዛብ ፡ መካከል ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ እንደሚወርድ ፡ ጠል ፥ በሣር ፡ ላይ ፡ እንደሚወርድ ፡ ካፊያ ፤ ሰውንም ፡ እንደማይጠብቅ ፥ የሰውንም ፡ ልጆች ፡ ተስፋ ፡ እንደማያደርግ ፡ ይኾናል ።

8 ፤ በዱር ፡ አራዊትም ፡ መካከል ፡ እንዳለ ፡ አንበሳ ፥ በበጎች ፡ መንጋም ፡ መካከል ፡ ዐልፎ ፡ እንደሚረግጥ ፥ የሚታደግም ፡ ሳይኖር ፡ እንደሚነጥቅ ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ደቦል ፥ እንዲሁ ፡ የያዕቆብ ፡ ቅሬታ ፡ በአሕዛብና ፡ በብዙ ፡ ወገኖች ፡ መካከል ፡ ይኾናል ።

9 ፤ እጅኽ ፡ በጠላቶችኽ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ትበል ፥ ጠላቶችኽም ፡ ኹሉ ፡ ይጥፉ ።

10 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ ፈረሶችኽን ፡ ከመካከልኽ ፡ አጠፋለኹ ፥ ሠረገላዎችኽንም ፡ እሰብራለኹ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤

11 ፤ የምድርኽንም ፡ ከተማዎች ፡ አጠፋለኹ ፥ ምሽጎችኽንም ፡ ኹሉ ፡ አፈርሳለኹ ፤

12 ፤ መተትንም ፡ ከእጅኽ ፡ አጠፋለኹ ፥ ሟርተኛዎችም ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አይኾኑልኽም ፤

13 ፤ የተቀረጹትን ፡ ምስሎችኽንና ፡ ሐውልቶችኽን ፡ ከመካከልኽ ፡ አጠፋለኹ ፥ ለእጅኽም ፡ ሥራ ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አትሰግድም ፤

14 ፤ የማምለኪያ ፡ ዐጸዶችኽንም ፡ ከመካከልኽ ፡ እነቅላለኹ ፥ ከተማዎችኽንም ፡ አፈርሳለኹ ።

15 ፤ ባልሰሙም ፡ አሕዛብ ፡ ላይ ፡ በቍጣና ፡ በመዓት ፡ እበቀላለኹ ።

ትንቢተ ፡ ሚክያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 6 ።

ምዕራፍ ፡ 6 ።

1 ፤ አኹን ፡– ተነሣ ፥ በተራራዎችም ፡ ፊት ፡ ተፋረድ ፥ ኰረብታዎችም ፡ ቃልኽን ፡ ይስሙ ፡ ብሎ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚለውን ፡ ስሙ ።

2 ፤ ተራራዎች ፡ ሆይ ፥ ጠንካራዎች ፡ የምድር ፡ መሠረቶችም ፡ ሆይ ፥ እግዚአብሔር ፡ ከሕዝቡ ፡ ጋራ ፡ ክርክር ፡ አለውና ፥ ከእስራኤልም ፡ ጋራ ፡ ይፋረዳልና ፥ የእግዚአብሔርን ፡ ክርክር ፡ ስሙ ።

3 ፤ ሕዝቤ ፡ ሆይ ፥ ምን ፡ አድርጌኻለኹ ፧ በምንስ ፡ አድክሜኻለኹ ፧ መስክርብኝ ።

4 ፤ ከግብጽ ፡ ምድር ፡ አውጥቼኻለኹ ፥ ከባርነት ፡ ቤትም ፡ ተቤዥቼኻለኹ ፤ በፊትኽም ፡ ሙሴንና ፡ አሮንን ፡ ማርያምንም ፡ ልኬልኽ ፡ ነበር ።

5 ፤ ሕዝቤ ፡ ሆይ ፥ የሞዐብ ፡ ንጉሥ ፡ ባላቅ ፡ የመከረውን ፥ የቢዖርም ፡ ልጅ ፡ በለዓም ፡ የመለሰለትን ፡ አኹን ፡ ዐስብ ፤ የእግዚአብሔርንም ፡ የጽድቅ ፡ ሥራ ፡ ታውቅ ፡ ዘንድ ፡ ከሰጢም ፡ ዠምሮ ፡ እስከ ፡ ገልገላ ፡ ድረስ ፡ ዐስብ ።

6 ፤ ምን ፡ ይዤ ፡ ወደእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ልምጣና ፡ በልዑል ፡ አምላክ ፡ ፊት ፡ ልስገድ ፧ የሚቃጠለውን ፡ መሥዋዕትና ፡ የአንዱን ፡ ዓመት ፡ ጥጃ ፡ ይዤ ፡ በፊቱ ፡ ልምጣን ፧

7 ፤ እግዚአብሔርስ ፡ በሺሕ ፡ አውራ ፡ በጎች ፡ ወይስ ፡ በእልፍ ፡ የዘይት ፡ ፈሳሾች ፡ ደስ ፡ ይለዋልን ፧ ወይስ ፡ የበኵር ፡ ልጄን ፡ ስለ ፡ በደሌ ፥ የሆዴንም ፡ ፍሬ ፡ ስለነፍሴ ፡ ኀጢአት ፡ እሰጣለኹን ፧

8 ፤ ሰው ፡ ሆይ ፥ መልካሙን ፡ ነግሮኻል ፤ እግዚአብሔርም ፡ ከአንተ ፡ ዘንድ ፡ የሚሻው ፡ ምንድር ፡ ነው ፧ ፍርድን ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ፥ ምሕረትንም ፡ ትወድ ፡ ዘንድ ፥ ከአምላክኽም ፡ ጋራ ፡ በትሕትና ፡ ትኼድ ፡ ዘንድ ፡ አይደለምን ፧

9 ፤ የእግዚአብሔር ፡ ድምፅ ፡ ከተማዪቱን ፡ ይጠራታል ፤ ስምኽን ፡ መፍራት ፡ ጥበብ ፡ ነው ፤ የመቅሠፍትን ፡ በትር ፥ ርሱንም ፡ ያዘጋጀ ፡ ማን ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ ስሙ ።

10 ፤ በእውኑ ፡ በኀጢአተኛ ፡ ቤት ፡ የኀጢአት ፡ መዝገብ ፥ የተጸየፈም ፡ ውሸተኛ ፡ መስፈሪያ ፡ ገና ፡ አለ ፡ ይኾን ፧

11 ፤ በአባይ ፡ ሚዛንና ፡ በከረጢት ፡ ባለ ፡ በተንኰል ፡ መመዘኛ ፡ ንጹሕ ፡ እኾናለኹን ፧

12 ፤ ባለጠጋዎቿን ፡ ግፍ ፡ ሞልቶባቸዋል ፤ በርሷም ፡ የሚኖሩ ፡ በሐሰት ፡ ተናግረዋል ፥ ምላሳቸውም ፡ በአፋቸው ፡ ውስጥ ፡ ተንኰለኛ ፡ ነው ።

13 ፤ ስለዚህ ፥ እኔ ፡ ደግሞ ፡ በክፉ ፡ ቍስል ፡ መታኹኽ ፤ ስለ ፡ ኀጢአትኽም ፡ አፈረስኹኽ ።

14 ፤ ትበላለኽ ፥ ነገር ፡ ግን ፥ አትጠግብም ፤ ችጋርኽም ፡ በመካከልኽ ፡ ይኾናል ፤ ትወስዳለኽ ፥ ነገር ፡ ግን ፥ አታድንም ፤ የምታድነውንም ፡ ለሰይፍ ፡ እሰጣለኹ ።

15 ፤ ትዘራለኽ ፥ ነገር ፡ ግን ፥ አታጭድም ፤ ወይራውንም ፡ ትጨምቃለኽ ፥ ነገር ፡ ግን ፥ ዘይቱን ፡ አትቀባም ፤ ወይኑንም ፡ ትጨምቃለኽ ፥ ነገር ፡ ግን ፥ የወይን ፡ ጠጁን ፡ አትጠጣም ።

16 ፤ አንተን ፡ ለጥፋት ፥ በርሷም ፡ የሚኖሩትን ፡ ለማፏጫ ፡ እሰጥ ፡ ዘንድ ፡ የዘንበሪን ፡ ሥርዐትና ፡ የአክአብን ፡ ቤት ፡ ሥራ ፡ ዅሉ ፡ ጠብቃችኋል ፥ በምክራቸውም ፡ ኼዳችኋል ፤ የሕዝቤንም ፡ ስድብ ፡ ትሸከማላችኹ ።

___________________ትንቢተ ፡ ሚክያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 7 ። ___________________

ምዕራፍ ፡ 7 ።

1 ፤ የዛፍ ፡ ፍሬና ፡ የወይን ፡ ፍሬ ፡ ከተለቀመ ፡ በኋላ ፡ እንደ ፡ ቀረው ፡ ቃርሚያ ፡ ኾኛለኹና ፡ ወዮልኝ! መብል ፡ የሚኾን ፡ ዘለላ ፥ ነፍሴም ፡ የተመኘችው ፡ በመዠመሪያ ፡ የበሰለው ፡ በለስ ፡ የለም ።

2 ፤ ደግ ፡ ሰው ፡ ከምድር ፡ ጠፍቷል ፥ በሰውም ፡ መካከል ፡ ቅን ፡ የለም ፤ ዅሉ ፡ ደምን ፡ ለማፍሰስ ፡ ያደባሉ ፥ ሰውም ፡ ዅሉ ፡ ወንድሙን ፡ በመረብ ፡ ለመያዝ ፡ ይከታተለዋል ።

3 ፤ እጆቻቸውን ፡ ለክፋት ፡ ያነሣሉ ፤ አለቃውና ፡ ፈራጁ ፡ ጉቦን ፡ ይፈልጋሉ ፥ ትልቁም ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ነፍሱ ፡ ምኞት ፡ ይናገራል ፤ እንዲሁም ፡ ክፋትን ፡ ይጐነጕናሉ ።

4 ፤ ከነርሱም ፡ ዅሉ ፡ የተሻለው ፡ ርሱ ፡ እንደ ፡ አሜከላ ፡ ነው ፥ ከዅሉም ፡ ቅን ፡ የኾነው ፡ እንደ ፡ ኵርንችት ፡ ነው ፤ ጠባቂዎችኽ ፡ የሚጐበኙበት ፡ ቀን ፡ መጥቷል ፤ አኹን ፡ ይሸበራሉ ።

5 ፤ ባልንጀራን ፡ አትመኑ ፥ በወዳጅም ፡ አትታመኑ ፤ የአፍኽን ፡ ደጅ ፡ በብብትኽ ፡ ከምትተኛው ፡ ጠብቅ ።

6 ፤ ወንድ ፡ ልጅ ፡ አባቱን ፡ ይንቃልና ፥ ሴት ፡ ልጅ ፡ በእናቷ ፡ ላይ ፥ ምራቲቱም ፡ በአማቷ ፡ ላይ ፡ ትነሣለችና ፥ የሰው ፡ ጠላቶች ፡ የቤቱ ፡ ሰዎች ፡ ናቸውና ።

7 ፤ እኔ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እመለከታለኹ ፥ የመድኀኒቴንም ፡ አምላክ ፡ ተስፋ ፡ አደርጋለኹ ፤ አምላኬም ፡ ይሰማኛል ።

8 ፤ ጠላቴ ፡ ሆይ ፥ ብወድቅ ፡ እነሣለኹና ፥ በጨለማም ፡ ብቀመጥ ፡ እግዚአብሔር ፡ ብርሃን ፡ ይኾንልኛልና ፥ በእኔ ፡ ላይ ፡ ደስ ፡ አይበልሽ ።

9 ፤ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ ኀጢአት ፡ ሠርቻለኹና ፡ እስኪ.ሟገትልኝ ፡ ድረስ ፥ ፍርድን ፡ ለእኔ ፡ እስኪ.ያደርግ ፡ ድረስ ፡ ቍጣውን ፡ እታገሣለኹ ። ወደ ፡ ብርሃን ፡ ያወጣኛል ፥ ጽድቅንም ፡ አያለኹ ።

10 ፤ ጠላቴም ፡ ታያለች ፥ እኔንም ፦ አምላክኽ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወዴት ፡ ነው ፡ ያለች ፡ በዕፍረት ፡ ትከደናለች ።

11 ፤ ዐይኖቼ ፡ ይመለከቷታል ፤ አኹን ፡ እንደ ፡ መንገድ ፡ ጭቃ ፡ ትረገጣለች ። ቅጥርሽ ፡ በሚሠራበት ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ድንበርሽ ፡ ትስፋፋለች ።

12 ፤ በዚያ ፡ ቀን ፡ ከአሶርና ፡ ከግብጽ ፡ ከተማዎች ፥ ከግብጽ ፡ እስከ ፡ ወንዙ ፥ ከባሕርም ፡ እስከ ፡ ባሕር ፥ ከተራራም ፡ እስከ ፡ ተራራ ፡ ድረስ ፡ ወደ ፡ አንቺ ፡ ይመጣሉ ።

13 ፤ ምድሪቱ ፡ ግን ፡ በሚኖሩባት ፡ በሥራቸው ፡ ፍሬ ፡ ምክንያት ፡ ባድማ ፡ ትኾናለች ።

14 ፤ በቀርሜሎስ ፡ መካከል ፡ ባለው ፡ ዱር ፡ ብቻቸውን ፡ የተቀመጡት ፡ ሰዎችኽ ፥ የርስትኽን ፡ በጎች ፥ በበትርኽ ፡ አግድ ፤ እንደ ፡ ቀደመውም ፡ ዘመን ፡ በበሳንና ፡ በገለዓድ ፡ ይሰማሩ ።

15 ፤ ከግብጽ ፡ ምድር ፡ እንደ ፡ ወጣኽበት ፡ ዘመን ፡ ተኣምራትን ፡ አሳያቸዋለኹ ።

16 ፤ አሕዛብ ፡ አይተው ፡ በጕልበታቸው ፡ ኹሉ ፡ ያፍራሉ ፤ እጃቸውን ፡ በአፋቸው ፡ ላይ ፡ ያኖራሉ ፥ ዦሯቸውም ፡ ትደነቍራለች ፤

17 ፤ እንደ ፡ እባብም ፡ መሬት ፡ ይልሳሉ ፥ እንደምድርም ፡ ተንቀሳቃሾች ፡ እየተንቀጠቀጡ ፡ ከግንባቸው ፡ ይመጣሉ ፤ ፈርተውም ፡ ወደ ፡ አምላካችን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይመጣሉ ፥ ስለ ፡ አንተም ፡ ይፈራሉ ።

18 ፤ በደልን ፡ ይቅር ፡ የሚል ፥ የርስቱንም ፡ ቅሬታ ፡ ዐመፅ ፡ የሚያሳልፍ ፡ እንደ ፡ አንተ ፡ ያለ ፡ አምላክ ፡ ማን ፡ ነው ፡ ምሕረትን ፡ ይወዳልና ፥ ቍጣውን ፡ ለዘለዓለም ፡ አይጠብቅም ።

19 ፤ ተመልሶ ፡ ይምረናል ፤ ክፋታችንንም ፡ ይጠቀጥቃል ፥ ኀጢአታችንንም ፡ በባሕሩ ፡ ጥልቅ ፡ ይጥለዋል ።

20 ፤ ከቀድሞ ፡ ዘመን ፡ ዠምረኽ ፡ ለአባቶቻችን ፡ የማልኽላቸውን ፡ እውነት ፡ ለያዕቆብ ፥ ምሕረትንም ፡ ለአብርሃም ፡ ታደርጋለኽ ❖

# ትንቢተ ፡ ዮናስ ።

(ክለሳ.1.20020507)

ትንቢተ ፡ ዮናስ ፤ ምዕራፍ ፡ 1 ።

ምዕራፍ ፡ 1 ።

1 ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደዐማቴ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ዮናስ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፦

2 ፤ ተነሥተኽ ፡ ወደዚያች ፡ ወደ ፡ ታላቂቱ ፡ ከተማ ፡ ወደ ፡ ነነዌ ፡ ኺድ ፤ ክፋታቸውም ፡ ወደ ፡ ፊቴ ፡ ወጥቷልና ፤ በርሷ ፡ ላይ ፡ ስበክ ።

3 ፤ ዮናስ ፡ ግን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ወደ ፡ ተርሴስ ፡ ይኰበልል ፡ ዘንድ ፡ ተነሣ ፤ ወደ ፡ ኢዮጴም ፡ ወረደ ፤ ወደ ፡ ተርሴስም ፡ የምታልፍ ፡ መርከብ ፡ አገኘ ፤ ከእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ኰብሎ ፡ ከነርሱ ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ ተርሴስ ፡ ይኼድ ፡ ዘንድ ፡ ዋጋ ፡ ሰጥቶ ፡ ወደ ፡ ርሷ ፡ ገባ ።

4 ፤ እግዚአብሔርም ፡ በባሕሩ ፡ ላይ ፡ ታላቅ ፡ ነፋስን ፡ አመጣ ፤ በባሕርም ፡ ላይ ፡ ታላቅ ፡ ማዕበል ፡ ኾነ ፤ መርከቢቱም ፡ ልትሰበር ፡ ቀረበች ።

5 ፤ መርከበኛዎቹም ፡ ፈሩ ፤ እያንዳንዱም ፡ ወደ ፡ አምላኩ ፡ ጮኸ ፤ መርከቢቱም ፡ እንድትቀልላቸው ፡ በውስጧ ፡ የነበረውን ፡ ዕቃ ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ጣሉት ፤ ዮናስ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ መርከቡ ፡ ውስጠኛው ፡ ክፍል ፡ ወርዶ ፡ ነበር ፤ በከባድ ፡ እንቅልፍም ፡ ተኝቶ ፡ ነበር ።

6 ፤ የመርከቡም ፡ አለቃ ፡ ወደ ፡ ርሱ ፡ ቀርቦ ፦ ምነው ፡ ተኝተኻል ፧ እንዳንጠፋ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያስበን ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ ተነሥተኽ ፡ አምላክኽን ፡ ጥራ ፡ አለው ።

7 ፤ ርስ ፡ በርሳቸውም ፦ ይህ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ በማን ፡ ምክንያት ፡ እንዳገኘን ፡ እናውቅ ፡ ዘንድ ፡ ኑ ፤ ዕጣ ፡ እንጣጣል ፡ ተባባሉ ። ዕጣም ፡ ተጣጣሉ ፤ ዕጣውም ፡ በዮናስ ፡ ላይ ፡ ወደቀ ።

8 ፤ የዚያን ፡ ጊዜም ፦ ይህ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ በማን ፡ ምክንያት ፡ እንዳገኘን ፡ እባክኽ ፡ ንገረን ፤ ሥራኽ ፡ ምንድር ፡ ነው ፧ ከወዴትስ ፡ መጣኽ ፧ አገርኽስ ፡ ወዴት ፡ ነው ፧ ወይስ ፡ ከማን ፡ ወገን ፡ ነኽ ፧ አሉት ።

9 ፤ ርሱም ፦ እኔ ፡ ዕብራዊ ፡ ነኝ ፤ ባሕሩንና ፡ የብሱን ፡ የፈጠረውን ፡ የሰማይን ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመልካለኊ ፡ አላቸው ።

10 ፤ እነዚያም ፡ ሰዎች ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ እንደ ፡ ኰበለለ ፡ ርሱ ፡ ስለ ፡ ነገራቸው ፡ ዐውቀዋልና ፤ እጅግ ፡ ፈርተው ፦ ይህ ፡ ያደረግኸው ፡ ምንድር ፡ ነው ፧ አሉት ።

11 ፤ ባሕሩንም ፡ ሞገዱ ፡ አጥብቆ ፡ ያናውጠው ፡ ነበርና ፦ ባሕሩ ፡ ከእኛ ፡ ዘንድ ፡ ጸጥ ፡ እንዲል ፡ ምን ፡ እናድርግብኽ ፧ አሉት ።

12 ፤ ርሱም ፦ ይህ ፡ ታላቅ ፡ ማዕበል ፡ በእኔ ፡ ምክንያት ፡ እንዳገኛችኊ ፡ ዐውቃለኊና ፡ አንሥታችኊ ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ጣሉኝ ፤ ባሕሩም ፡ ጸጥ ፡ ይልላችኋል ፡ አላቸው ።

13 ፤ ሰዎቹ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ምድሩ ፡ ሊመለሱ ፡ አጥብቀው ፡ ቀዘፉ ፤ ዳሩ ፡ ግን ፡ ባሕሩ ፡ እጅግ ፡ አብዝቶ ፡ ይናወጥባቸው ፡ ነበርና ፤ አልቻሉም ።

14 ፤ ስለዚህ ፤ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኸው ፦ አቤቱ ፤ እንደ ፡ ወደድኽ ፡ አድርገኻልና ፤ እንለምንኻለን ፤ አቤቱ ፤ ስለዚህ ፡ ሰው ፡ ነፍስ ፡ እንዳንጠፋ ፡ ንጹሕም ፡ ደም ፡ በእኛ ፡ ላይ ፡ እንዳታደርግ ፡ እንለምንኻለን ፡ አሉ ።

15 ፤ ዮናስንም ፡ ወስደው ፡ ወደ ፡ ባሕሩ ፡ ጣሉት ፤ ባሕሩም ፡ ከመናወጡ ፡ ጸጥ ፡ አለ ።

16 ፤ ሰዎችም ፡ እግዚአብሔርን ፡ እጅግ ፡ ፈሩ ፤ ለእግዚአብሔርም ፡ መሥዋዕትን ፡ አቀረቡ ፤ ስእለትንም ፡ ተሳሉ ።

ትንቢተ ፡ ዮናስ ፥ ምዕራፍ ፡ 2 ።

ምዕራፍ ፡ 2 ።

1 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ዮናስን ፡ የሚውጥ ፡ ታላቅ ፡ ዓሣ ፡ አሰናዳ ፤ ዮናስም ፡ ሦስት ፡ ቀንና ፡ ሦስት ፡ ሌሊት ፡ በዓሣው ፡ ሆድ ፡ ውስጥ ፡ ነበረ ።

2 ፤ ዮናስም ፡ በዓሣው ፡ ሆድ ፡ ውስጥ ፡ ኾኖ ፡ ወደ ፡ አምላኩ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጸለየ ፥ እንዲህም ፡ አለ ፦

3 ፤ በመከራዬ ፡ ሳለኹ ፡ ወደ ፡ አምላኬ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኽኹ ፥ ርሱም ፡ ሰማኝ ፤ በሲኦልም ፡ ሆድ ፡ ውስጥ ፡ ኾኜ ፡ ጮኽኹ ፥ ቃሌንም ፡ አዳመጥኽ ።

4 ፤ ወደ ፡ ጥልቁ ፡ ወደ ፡ ባሕሩ ፡ ውስጥ ፡ ጣልኸኝ ፥ ፈሳሾችም ፡ በዙሪያዬ ፡ ነበሩ ፤ ማዕበልኽና ፡ ሞገድኽ ፡ ኹሉ ፡ በላዬ ፡ ዐለፉ ።

5 ፤ እኔም ፦ ከዐይንኽ ፡ ፊት ፡ ተጣልኹ ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ወደ ፡ ቅዱስ ፡ መቅደስኽ ፡ ደግሞ ፡ እመለከታለኹ ፡ አልኹ ።

6 ፤ ውሃዎችም ፡ እስከ ፡ ነፍሴ ፡ ድረስ ፡ ከበቡኝ ፤ ጥልቁ ፡ ባሕር ፡ በዙሪያዬ ፡ ነበረ ፤ የባሕሩ ፡ ሣር ፡ በራሴ ፡ ተጠምጥሞ ፡ ነበር ።

7 ፤ ወደተራራዎች ፡ መሠረት ፡ ወረድኹ ፤ በምድርና ፡ በመወርወሪያዎቿ ፡ ለዘለዓለም ፡ ተዘጋኹ ፤ አንተ ፡ ግን ፥ አቤቱ ፡ አምላኬ ፥ ሕይወቴን ፡ ከጕድጓዱ ፡ አወጣኽ ።

8 ፤ ነፍሴ ፡ በዛለችብኝ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ዐሰብኹት ፤ ጸሎቴም ፡ ወዳንተ ፡ ወደ ፡ ቅዱስ ፡ መቅደስኽ ፡ ገባች ።

9 ፤ ከንቱነትንና ፡ ሐሰትን ፡ የሚጠብቁ ፡ ምሕረታቸውን ፡ ትተዋል ።

10 ፤ እኔ ፡ ግን ፡ በምስጋና ፡ ቃል ፡ እሠዋልኻለኹ ፤ የተሳልኹትንም ፡ እከፍላለኹ ። ደኅንነት ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ነው ።

11 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ዓሣውን ፡ አዘዘው ፥ ርሱም ፡ ዮናስን ፡ በየብስ ፡ ላይ ፡ ተፋው ።

ትንቢተ ፡ ዮናስ ፥ ምዕራፍ ፡ 3 ።

ምዕራፍ ፡ 3 ።

1 ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ኹለተኛ ፡ ወደ ፡ ዮናስ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፦

2 ፤ ተነሥተኽ ፡ ወደዚያች ፡ ወደ ፡ ታላቂቱ ፡ ከተማ ፡ ወደ ፡ ነነዌ ፡ ኺድ ፥ የምነግርኽንም ፡ ስብከት ፡ ስበክላት ፡ አለው ።

3 ፤ ዮናስም ፡ ተነሥቶ ፡ እንደእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ ነነዌ ፡ ኼደ ፤ ነነዌም ፡ የሦስት ፡ ቀን ፡ መንገድ ፡ ያኽል ፡ እጅግ ፡ ታላቅ ፡ ከተማ ፡ ነበረች ።

4 ፤ ዮናስም ፡ የአንድ ፡ ቀን ፡ መንገድ ፡ ያኽል ፡ ወደ ፡ ከተማዪቱ ፡ ውስጥ ፡ ሊገባ ፡ ዠመረ ፤ ጮኾም ፦ በሦስት ፡ ቀን ፡ ውስጥ ፡ ነነዌ ፡ ትገለበጣለች ፡ አለ ።

5 ፤ የነነዌም ፡ ሰዎች ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመኑ ፤ ለጾም ፡ ዐዋጅ ፡ ነገሩ ፥ ከታላቁም ፡ ዠምሮ ፡ እስከ ፡ ታናሹ ፡ ድረስ ፡ ማቅ ፡ ለበሱ ።

6 ፤ ወሬውም ፡ ወደነነዌ ፡ ንጉሥ ፡ ደረሰ ፤ ርሱም ፡ ከዙፋኑ ፡ ተነሥቶ ፡ መጐናጸፊያውን ፡ አወለቀ ፡ ማቅም ፡ ለበሰ ፥ በዐመድም ፡ ላይ ፡ ተቀመጠ ።

7 ፤ ዐዋጅም ፡ አስነገረ ፥ በነነዌም ፡ ውስጥ ፡ የንጉሡንና ፡ የመኳንንቱን ፡ ትእዛዝ ፡ አሳወጀ ፥ እንዲህም ፡ አለ ፦ ሰዎችና ፡ እንስሳዎች ፡ ላሞችና ፡ በጎች ፡ አንዳችን ፡ አይቅመሱ ፤ አይሰማሩም ፡ ውሃንም ፡ አይጠጡ ፤

8 ፤ ሰዎችና ፡ እንስሳዎችም ፡ በማቅ ፡ ይከደኑ ፥ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ በብርቱ ፡ ይጩኹ ፤ ሰዎችም ፡ ኹሉ ፡ ከክፉ ፡ መንገዳቸውና ፡ በእጃቸው ፡ ካለው ፡ ግፍ ፡ ይመለሱ ።

9 ፤ እኛ ፡ እንዳንጠፋ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተመልሶ ፡ ይጸጸት ፡ እንደ ፡ ኾነ ፥ ከጽኑ ፡ ቍጣውም ፡ ይመለስ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ ማን ፡ ያውቃል ፧

10 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ከክፉ ፡ መንገዳቸው ፡ እንደተመለሱ ፡ ሥራቸውን ፡ አየ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ያደርግባቸው ፡
ዘንድ ፡ በተናገረው ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ተጸጸቶ ፡ አላደረገውም ።

ትንቢተ ፡ ዮናስ ፥ ምዕራፍ ፡ 4 ።

ምዕራፍ ፡ 4 ።

1 ፤ ይህም ፡ ዮናስን ፡ ክቶ ፡ ደስ ፡ አላሠኘውም ፥ ርሱም ፡ ተቈጣ ።

2 ፤ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ጸለየና ፦ አቤቱ ፥ እለምንኻለኹ ፤ በአገሬ ፡ ሳለኹ ፡ የተናገርኹት ፡ ይህ ፡
አልነበረምን ፥ አንተ ፡ ቸርና ፡ ይቅር ፡ ባይ ፥ ታጋሽም ፥ ምሕረትኽም ፡ የበዛ ፥ ከክፉው ፡ ነገርም ፡ የተነሣ ፡ የምትጸጸት ፡
አምላክ ፡ እንደ ፡ ኾንኽ ፡ ዐውቄ ፡ ነበርና ፥ ስለዚህ ፡ ወደ ፡ ተርሴስ ፡ ለመኰብለል ፡ ፈጥኜ ፡ ነበር ።

3 ፤ አኹንም ፥ አቤቱ ፥ ከሕይወት ፡ ሞት ፡ ይሻለኛልና ፥ እባክኽ ፥ ነፍሴን ፡ ከእኔ ፡ ውሰድ ፡ አለው ።

4 ፤ እግዚአብሔርም ፦ በእውኑ ፡ ትቈጣ ፡ ዘንድ ፡ ይገ፟ባ፟ኻልን ፥ አለ ።

5 ፤ ዮናስም ፡ ከከተማዪቱ ፡ ወጣ ፥ ከከተማዪቱም ፡ በስተምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ተቀመጠ ፤ ከተማዪቱንም ፡ የሚያገኛትን ፡
እስኪያይ ፡ ድረስ ፡ በዚያ ፡ ለራሱ ፡ ዳስ ፡ ሠርቶ ፡ ከጥላው ፡ በታች ፡ ተቀመጠ ።

6 ፤ እግዚአብሔር ፡ አምላክም ፡ ቅል ፡ አዘጋጀ ፥ ከጭንቀቱም ፡ ታድነው ፡ ዘንድ ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ጥላ ፡ እንድትኾን ፡
በዮናስ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረጋት ፤ ዮናስም ፡ ስለ ፡ ቅሊቱ ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ አለው ።

7 ፤ በነጋው ፡ ግን ፡ ወገግ ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ትልን ፡ አዘጋጀ ፥ ርሷም ፡ ቅሊቱን ፡ እስክትደርቅ ፡ ድረስ ፡
መታቻት ።

8 ፤ ፀሓይም ፡ በወጣች ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ትኵስ ፡ የምሥራቅ ፡ ነፋስ ፡ አዘጋጀ ፡ ዮናስ ፡ እስኪዝል ፡ ድረስም ፡ ፀሓይ ፡
ራሱን ፡ መታው ፤ ለራሱም ፡ ሞትን ፡ ፈለገና ፦ ከሕይወት ፡ ሞት ፡ ይሻለኛል ፡ አለ ።

9 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ዮናስን ፦ በእውኑ ፡ ስለዚች ፡ ቅል ፡ ትቈጣ ፡ ዘንድ ፡ ይገ፟ባ፟ኻልን ፥ አለው ። ርሱም ፦ እስከ ፡
ሞት ፡ ድረስ ፡ እቈጣ ፡ ዘንድ ፡ ይገ፟ባ፟ኛል ፡ አለ ።

10 ፤ እግዚአብሔርም ፦ አንተ ፡ ትበቅል ፡ ዘንድ ፡ ላልደከምኽባት ፡ ላላሳደግኻትም ፥ ባንድ ፡ ሌሊት ፡ ለበቀለች ፥ ባንድ ፡
ሌሊትም ፡ ለደረቀችው ፡ ቅል ፡ አዝነኻል ።

11 ፤ እኔስ ፡ ቀኛቸውንና ፡ ግራቸውን ፡ የማይለዩ ፡ ከመቶ ፡ ኻያ ፡ ሺሕ ፡ የሚበልጡ ፡ ሰዎችና ፡ ብዙ ፡ እንስሳዎች ፡
ላሉባት ፡ ለታላቂቱ ፡ ከተማ ፡ ለነነዌ ፡ አላዝንምን ፥ አለው ፨

# ትንቢተ ፡ ዕንባቆም ።

(ክለሳ.1.20020507)

ትንቢተ ፡ ዕንባቆም ፥ ምዕራፍ ፡ 1 ።

ምዕራፍ ፡ 1 ።

1 ፤ ነቢዩ ፡ ዕንባቆም ፡ ያየው ፡ ሸክም ፡ ይህ ፡ ነው ።

2 ፤ አቤቱ ፥ እኔ ፡ ስጮኽ ፡ የማትሰማው ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ነው ፤ ስለ ፡ ግፍ ፡ ወዳንተ ፡ እጮኻለኹ ፥ አንተም ፡ አታድንም ።

3 ፤ በደልንስ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ አሳየኸኝ ፤ ጠማምነትንስ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ትመለከታለኽ ፤ ጥፋትና ፡ ግፍ ፡ በፊቴ ፡ ነው ፤ ጠብና ፡ ክርክር ፡ ይነሣሉ ።

4 ፤ ስለዚህ ፥ ሕግ ፡ ላልቷል ፥ ፍርድም ፡ ድል ፡ ነሥቶ ፡ አይወጣም ፤ ኀጢአተኛ ፡ ጻድቅን ፡ ይከባልና ፤ ስለዚህ ፥ ፍርድ ፡ ጠማማ ፡ ኾኖ ፡ ይወጣል ።

5 ፤ እናንተ ፡ የምትንቁ ፡ ሆይ ፥ አንድ ፡ ቢተርክላችኹ ፡ ስንኳ ፡ የማታምኑትን ፡ ሥራ ፡ በዘመናችኹ ፡ እሠራለኹና ፡ እዩ ፥ ተመልከቱ ፥ ተደነቁ ።

6 ፤ እንሆ ፥ የእነርሱ ፡ ያልኾነውን ፡ መኖሪያ ፡ ይወርሱ ፡ ዘንድ ፡ በምድር ፡ ስፋት ፡ ላይ ፡ የሚኼዱትን ፡ መራሮችንና ፡ ፈጣኖችን ፡ ሕዝብ ፡ ከለዳውያንን ፡ አስነሣለኹ ።

7 ፤ እነርሱ ፡ የሚያስፈሩና ፡ የሚያስደነግጡ ፡ ናቸው ፤ ፍርዳቸውና ፡ ክብራቸው ፡ ከራሳቸው ፡ ይወጣል ።

8 ፤ ፈረሶቻቸውም ፡ ከነብር ፡ ይልቅ ፡ ፈጣኖች ፡ ናቸው ፥ ከማታም ፡ ተኵላ ፡ ይልቅ ፡ ጨካኞች ፡ ናቸው ፤ ፈረሰኞዎቻቸውም ፡ ይንሳፈፋሉ ፥ ከሩቅም ፡ ይመጣሉ ፥ ለመብልም ፡ እንደሚቸኵል ፡ ንስር ፡ ይበራሉ ።

9 ፤ ኹሉም ፡ ለግፍ ፡ ሥራ ፡ ይመጣሉ ፥ ፊታቸውንም ፡ እንደ ፡ ምሥራቅ ፡ ነፋስ ፡ ያቀናሉ ፤ ምርኮኞዎችንም ፡ እንደ ፡ አሸዋ ፡ ይሰበስባሉ ።

10 ፤ በነገሥታት ፡ ላይ ፡ ያላግጣሉ ፥ መሳፍንትም ፡ ዋዛ ፡ ኾነውላቸዋል ፤ በምሽጉ ፡ ኹሉ ፡ ይሥቃሉ ፥ ዐፈሩንም ፡ ከምረው ፡ ይወስዱታል ።

11 ፤ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ እንደ ፡ ነፋስ ፡ ዐልፎ ፡ ይኼዳል ፥ ይበድልማል ፤ ኀይሉንም ፡ አምላክ ፡ ያደርገዋል ።

12 ፤ አቤቱ ፥ የተቀደስኽ ፡ አምላኬ ፡ ሆይ ፥ አንተ ፡ ከዘለዓለም ፡ ዠምሮ ፡ አልነበርኽምን ፤ እኛ ፡ አንሞትም ፤ አቤቱ ፥ ለፍርድ ፡ ሠርተኸዋል ፥ ለተግሣጽም ፡ አድርገኸዋል ።

13 ፤ ዐይኖችኽ ፡ ክፉ ፡ እንዳያዩ ፡ ንጹሓን ፡ ናቸው ፥ ጠማምነትንም ፡ ትመለከት ፡ ዘንድ ፡ አትችልም ፤ አታላዮችንስ ፡ ለምን ፡ ትመለከታለኽ ፤ ኀጢአተኛውስ ፡ ከርሱ ፡ ይልቅ ፡ ጻድቅ ፡ የኾነውን ፡ ሲውጠው ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ዝም ፡ ትላለኽ ፤

14 ፤ ሰዎችንም ፡ እንደ ፡ ባሕር ፡ ዓሣዎች ፥ አለቃም ፡ እንደሌላቸው ፡ ተንቀሳቃሾች ፡ ለምን ፡ ታደርጋቸዋለኽ ፤

15 ፤ ኹሉን ፡ በመቃጥን ፡ ያወጣል ፥ በመረቡም ፡ ይይዛቸዋል ፥ በአሽክላውም ፡ ውስጥ ፡ ያከማቻቸዋል ፤ ስለዚህ ፥ ደስ ፡ እያለው ፡ እልል ፡ ይላል ።

16 ፤ ዕድል ፡ ፈንታው ፡ በእነርሱ ፡ ሰብታለችና ፥ መብሉም ፡ በዝቷልና ፥ ስለዚህ ፡ ለመረቡ ፡ ይሠዋል ፥ ለአሽክላውም ፡ ያጥናል ።

17 ፤ ስለዚህ ፥ መረቡን ፡ ይጥላልን ፤ አሕዛብንም ፡ ዘወትር ፡ ይገድል ፡ ዘንድ ፡ አይራራምን ፤

ትንቢተ ፡ ዕንባቆም ፥ ምዕራፍ ፡ 2 ።

ምዕራፍ ፡ 2 ።

1 ፤ በመጠበቂያዬ ፡ ላይ ፡ እቆማለኹ ፥ በዐምባ ፡ ላይም ፡ እወጣለኹ ፤ የሚናገረኝንም ፥ ስለ ፡ ክርክሬም ፡ የምመልሰውን ፡ ዐውቅ ፡ ዘንድ ፡ እመለከታለኹ ።

2 ፤ እግዚአብሔርም ፡ መለሰልኝ ፡ እንዲህም ፡ አለ ፦ አንባቢው ፡ ይፈጥን ፡ ዘንድ ፡ ራእዩን ፡ ጻፍ ፥ በጽላትም ፡ ላይ ፡ ግለጠው ።

3 ፤ ራእዩ ፡ ገና ፡ እስከተወሰነው ፡ ጊዜ ፡ ነው ፥ ወደ ፡ ፍጻሜውም ፡ ይቸኰላል ፥ ርሱም ፡ አይዋሽም ፤ ቢዘገይም ፡ በርግጥ ፡ ይመጣልና ፥ ታገሠው ፤ ርሱ ፡ አይዘገይም ።

4 ፤ እንሆ ፥ ነፍሱ ፡ ኵርታለች ፥ በውስጡም ፡ ቅን ፡ አይደለችም ፤ ጻድቅ ፡ ግን ፡ በእምነቱ ፡ በሕይወት ፡ ይኖራል ።

5 ፤ ርሱ ፡ አታላይና ፡ ኵሩ ፡ ሰው ፡ ነው ፤ በሰፍራው ፡ ዐርፎ ፡ አይቀመጥም ፤ ሥሥቱን ፡ እንደ ፡ሲኦል ፡ ያሰፋል ፥ ርሱም ፡ እንደ ፡ ሞት ፡ አይጠግብም ፤ አሕዛብንም ፡ ኹሉ ፡ ወደ ፡ ርሱ ፡ ይሰበስባል ፥ ወገኖቹንም ፡ ኹሉ ፡ ወደ ፡ ርሱ ፡ ያከማቻል ።

6 ፤ እነዚህ ፡ ኹሉ ፦ ለርሱ ፡ ያልኾነውን ፡ ወደ ፡ ርሱ ፡ ለሚሰበስብ ፡ መያዣውንም ፡ ለራሱ ፡ የሚያበዛ ፡ ወዮለት! እስከ ፡ መቼ ፡ ነው ፡ እያሉ ፡ ምሳሌ ፡ አይመስሉበትምን ፡

7 ፤ ተረትም ፡ አይተርቱበትምን ፡ የሚነክሱኽ ፡ ድንገት ፡ አይነሡብኽምን ፡ የሚያስጨንቁኽም ፡ ይነቃሉ ፤ ለእነርሱም ፡ ብዝበዛ ፡ ትኾናለኽ ።

8 ፤ የሰውን ፡ ደም ፡ ስላፈሰስኽ ፥ በምድሪቱና ፡ በከተማዪቱም ፡ በርሷም ፡ በሚኖሩ ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፡ ስላደረግኸው ፡ ግፍ ፥ አንተ ፡ ብዙዎችን ፡ አሕዛብን ፡ በዝብዘኻልና ፥ ከአሕዛብ ፡ የቀሩት ፡ ኹሉ ፡ ይበዘብዙኻል ።

9 ፤ ከክፉ ፡ እንዲድን ፡ ጐጆውን ፡ በከፍታ ፡ ላይ ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ ለቤቱ ፡ ክፉ ፡ ትርፍን ፡ ለሚሰበስብ ፡ ወዮለት!

10 ፤ ብዙ ፡ አሕዛብን ፡ አጥፍተኻልና ፥ ለቤትኽ ፡ ዕፍረትን ፡ መክረኻል ፥ በነፍስኽም ፡ ላይ ፡ ኀጢአትን ፡ አድርገኻል ።

11 ፤ ድንጋይም ፡ ከግንብ ፡ ውስጥ ፡ ይጮኻል ፥ ዕንጨትም ፡ ከውቅር ፡ ውስጥ ፡ ይመልስለታል ።

12 ፤ ከተማን ፡ በደም ፡ ለሚሠራ ፥ ከተማንም ፡ በኀጢአት ፡ ለሚመሠርት ፡ ወዮለት!

13 ፤ እንሆ ፥ አሕዛብ ፡ ስለ ፡ እሳት ፡ እንዲሠሩ ፥ ወገኖችም ፡ ስለ ፡ ከንቱነት ፡ እንዲደክሙ ፡ ከሰራዊት ፡ ጌታ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የኾነ ፡ አይደለምን ፡

14 ፤ ውሃ ፡ ባሕርን ፡ እንደሚከድን ፥ ምድር ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ክብር ፡ በማወቅ ፡ ትሞላለችና ።

15 ፤ ኀፍረተ ፡ ሥጋውን ፡ ለማየት ፡ ባልንጀራውን ፡ ለሚያጠጣ ፥ ክፉንም ፡ ለሚጨምርበት ፥ ለሚያሰክረውም ፡ ወዮለት!

16 ፤ በክብር ፡ ፋንታ ፡ ዕፍረት ፡ ሞልቶብኻል ፤ አንተ ፡ ደግሞ ፡ ጠጥተኽ ፡ ተንገድገድ ፤ የእግዚአብሔር ፡ የቀኙ ፡ ጽዋ ፡ ይመለስብኻል ፥ ዕፍረትም ፡ በክብርኽ ፡ ላይ ፡ ይኾናል ።

17 ፤ የሰውንም ፡ ደም ፡ ስላፈሰስኽ ፥ በምድሪቱና ፡ በከተማዪቱም ፡ በርሷም ፡ በሚኖሩ ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፡ ስላደረግኸው ፡ ግፍ ፥ በሊባኖስ ፡ ላይ ፡ የሠራኸው ፡ ግፍ ፡ ይከድንኻል ፤ የአራዊትም ፡ አደጋ ፡ ያስፈራራኻል ።

18 ፤ የተቀረጸውን ፡ ምስል ፡ ሠሪው ፡ የቀረጸው ፡ ለምን ፡ ጥቅም ፡ ነው ፡ ዲዳንም ፡ ጣዖት ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ ሠሪው ፡ የታመነበቱ ፥ ሐሰትን ፡ የሚያስተምር ፡ ቀልጦ ፡ የተሠራ ፡ ምን ፡ ይጠቅማል ፡

19 ፤ ዕንጨቱን ፦ ንቃ ፥ ዲዳውንም ፡ ድንጋይ ፦ ተነሣ ፡ ለሚለው ፡ ወዮለት! በእውኑ ፡ ይህ ፡ ያስተምራልን ፡ እንሆ ፥ በወርቅና ፡ በብር ፡ ተለብጧል ፥ ምንም ፡ እስትንፋስ ፡ የለበትም ።

20 ፤ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ በተቀደሰ ፡ መቅደሱ ፡ አለ ፤ ምድርም ፡ ኹሉ ፡ በፊቱ ፡ ዝም ፡ ትበል ።

## ትንቢተ ፡ ዕንባቆም ፥ ምዕራፍ ፡ 3 ።

ምዕራፍ ፡ 3 ።

1 ፤ የነቢዩ ፡ የዕንባቆም ፡ ጸሎት ፡ በመዝሙር ።

2 ፤ አቤቱ ፥ ዝናኽን ፡ ሰምቼ ፡ ፈራኹ ፤ አቤቱ ፥ በዓመታት ፡ መካከል ፡ ሥራኽን ፡ ፈጽም ፤ በዓመታት ፡ መካከል ፡ ትታወቅ ፤ በመዓት ፡ ጊዜ ፡ ምሕረትን ፡ ዐስብ ።

3 ፤ እግዚአብሔር ፡ ከቴማን ፥ ቅዱሱም ፡ ከፋራን ፡ ተራራ ፡ ይመጣል ። ክብሩ ፡ ሰማያትን ፡ ከድኗል ፥ ምስጋናውም ፡
ምድርን ፡ሞልቷል ።

4 ፤ ጸዳሉም ፡ እንደ ፡ ብርሃን ፡ ነው ፤ ጨረር ፡ ከእጁ ፡ ወጥቷል ፤ ኀይሉም ፡ በዚያ ፡ ተሰውሯል ።

5 ፤ ቸነፈር ፡ በፊቱ ፡ ይኼዳል ፥ የእሳትም ፡ ነበልባል ፡ ከእግሩ ፡ ይወጣል ።

6 ፤ ቆመ ፥ ምድርንም ፡ አወካት ፤ ተመለከተ ፥ አሕዛብንም ፡ አናወጠ ፤ የዘለዓለምም ፡ ተራራዎች ፡
ተቀጠቀጡ ፥ የዘለዓለምም ፡ ኰረብታዎች ፡ ቀለጡ ፤ መንገዱ ፡ ከዘለዓለም ፡ ነው ።

7 ፤ የኢትዮጵያ ፡ ድንኳኖች ፡ሲጨነቁ ፡ አየኹ ፤ የምድያም ፡ አገር ፡ መጋረጃዎች ፡ ተንቀጠቀጡ ።

8 ፤ በእውኑ ፡ እግዚአብሔር ፡ በወንዞች ፡ ላይ ፡ ተቈጥቷልን ፧ ቍጣኽ ፡ በወንዞች ፡ ላይ ፥ መዓትኽም ፡ በባሕር ፡ ላይ ፡
ነውን ፧ በፈረሶችኽና ፡ በማዳንኽ ፡ ሠረገላዎች ፡ ላይ ፡ ተቀምጠኻልና ።

9 ፤ በቃልኽ ፡ እንደ ፡ ማልኽ ፡ መቅሠፍትኽን ፡ አወጣኽ ፤ ቀስትኽንም ፡ ገተርኽ ፤ ምድርን ፡ሰንጥቀኽ ፡ ፈሳሾችን ፡
አወጣኽ ።

10 ፤ ተራራዎች ፡ አንተን ፡ አይተው ፡ ተጨነቁ ፤ የውሃ ፡ ሞገድ ፡ ዐልፏል ፤ ቀላዩም ፡ ድምፁን ፡ ሰጥቷል ፥ እጁንም ፡
ወደ ፡ ላይ ፡ አንሥቷል ።

11 ፤ ፍላጻዎችኽ ፡ ከወጡበት ፡ ብርሃን ፡ የተነሣ ፥ ከሚንቦገቦገውም ፡ ከጦርኽ ፡ ጸዳል ፡ የተነሣ ፥ ፀሓይና ፡ ጨረቃ ፡
በመኖሪያቸው ፡ ቆሙ ።

12 ፤ በምድር ፡ ላይ ፡ በመዓት ፡ ተራመድኽ ፤ አሕዛብን ፡ በቍጣ ፡ አኼድኻቸው ።

13 ፤ ሕዝብኽን ፡ ለመታደግ ፥ የቀባኸውንም ፡ ለማዳን ፡ ወጣኽ ፤ የኀጢአተኛውን ፡ ቤት ፡ ራስ ፡
ቀጠቀጥኽ ፤ መሠረቱን ፡ እስከ ፡ ዐንገቱ ፡ ድረስ ፡ገለጥኽ ።

14 ፤ የአለቃዎችን ፡ ራስ ፡ በገዛ ፡ በትራቸው ፡ ወጋኽ ፤ እኔን ፡ ይበትኑ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስ ፡
መጡ ፤ ችግረኛውን ፡ በስውር ፡ ለመዋጥ ፡ ደስታቸው ፡ ነው ።

15 ፤ ፈረሶችኽን ፡ በባሕር ፥ በብዙ ፡ ውሃዎችም ፡ ላይ ፡ አስረገጥኽ ።

16 ፤ እኔ ፡ ሰምቻለኹ ፥ ልቤም ፡ ደነገጠብኝ ፤ ከድምፁ ፡ የተነሣ ፡ ከንፈሮቼ ፡ ተንቀጠቀጡ ፤ መንቀጥቀጥ ፡ ወደ ፡
ዐጥንቶቼ ፡ ውስጥ ፡ ገባ ፤ በስፍራዬ ፡ ኾኜ ፡ ተናወጥኹ ፤ በሚያስጨንቁን ፡ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ እስኪመጣ ፡ ድረስ ፡
የመከራን ፡ ቀን ፡ ዝም ፡ ብዬ ፡ እጠብቃለኹ ።

17 ፤ ምንም ፡ እንኳ ፡ በለስም ፡ ባታፈራ ፥ በወይንም ፡ሐረግ ፡ ፍሬ ፡ ባይገኝ ፥ የወይራ ፡ ሥራ ፡ ቢጐድል ፥ ዕርሾችም ፡
መብልን ፡ ባይሰጡ ፥ በጎች ፡ ከበረቱ ፡ ቢጠፉ ፥ ላሞችም ፡ በጋጡ ፡ ውስጥ ፡ ባይገኙ ፥

18 ፤ እኔ ፡ ግን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፤ በመድኀኒቴ ፡ አምላክ ፡ ሐሤት ፡ አደርጋለኹ ።

19 ፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ኀይሌ ፡ ነው ፤ እግሮቼን ፡ እንደ ፡ ዋላ ፡ እግሮች ፡ ያደርጋል ፤ በከፍታዎችም ፡ ላይ ፡
ያስኼደኛል ፨

# ትንቢተ ፡ ሶፎንያስ ።

(ክለሳ.1.20020507)

ትንቢተ ፡ ሶፎንያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 1 ።

ምዕራፍ ፡ 1 ።

1 ፤ በይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ በዓሞጽ ፡ ልጅ ፡ በኢዮስያስ ፡ ዘመን ፡ ወደሕዝቅያስ ፡ ልጅ ፡ ወደአማርያ ፡ ልጅ ፡ ወደጎዶልያስ ፡
ልጅ ፡ ወደኵሲ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ሶፎንያስ[271] ፡ የመጣ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ፦

2 ፤ ነገርን ፡ ኹሉ ፡ ከምድር ፡ ፊት ፡ ፈጽሜ ፡ አጠፋለኹ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

3 ፤ ሰውንና ፡ እንስሳን ፡ አጠፋለኹ ፤ የሰማይን ፡ ወፎችና ፡ የባሕርን ፡ ዓሣዎች ፡ ማሰናከያንም ፡ ከኀጢአተኛዎች ፡ ጋራ ፡
አጠፋለኹ ፤ ሰውንም ፡ ከምድር ፡ ፊት ፡ እቈርጣለኹ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

4 ፤ እጄንም ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ በሚኖሩት ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፡ እዘረጋለኹ ፤ ከዚህም ፡ ስፍራ ፡ የበዓልን ፡
ቅሬታና ፡ የጣዖታቱን ፡ ካህናት ፡ ስም ፡ አጠፋለኹ ፤

5 ፤ በሰገነትም ፡ ላይ ፡ ለሰማይ ፡ ሰራዊት ፡ የሚሰግዱትን ፥ በእግዚአብሔርና ፡ በንጉሣቸው ፡ በሚልኮም ፡ ምለው ፡
የሚሰግዱትን ፥

6 ፤ እግዚአብሔርንም ፡ ከመከተል ፡ የተመለሱትን ፥ እግዚአብሔርንም ፡ ያልፈለጉትንና ፡ ያልጠየቁትን ፡ አጠፋለኹ ።

7 ፤ የእግዚአብሔር ፡ ቀን ፡ ቀርቧልና ፥ እግዚአብሔር ፡ መሥዋዕትን ፡ አዘጋጅቷልና ፥ የጠራቸውንም ፡
ቀድሷልና ፥ በጌታ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ዝም ፡ በሉ ።

8 ፤ በእግዚአብሔርም ፡ መሥዋዕት ፡ ቀን ፡ አለቃዎችንና ፡ የንጉሥን ፡ ልጆች ፡ እንግዳ ፡ ልብስ ፡ የሚለብሱትንም ፡ ኹሉ ፡
እቀጣለኹ ።

9 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ በመድረኩ ፡ ላይ ፡ የሚዘሉትን ፥ የጌታቸውን ፡ ቤት ፡ ዐመፃንና ፡ ሽንገላን ፡ የሚሞሉትን ፡
እቀጣለኹ ።

10 ፤ በዚያ ፡ ቀን ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፥ ከዓሣው ፡ በር ፡ የጩኸት ፡ ድምፅ ፥ ከከተማውም ፡ በኹለተኛው ፡ ክፍል ፡
ውካታ ፥ ከኰረብታዎቹም ፡ ታላቅ ፡ ሽብር ፡ ይኾናል ።

11 ፤ እናንተ ፡ በመክቴሽ ፡ የምትኖሩ ፡ ሆይ ፥ የከነዓን ፡ ሕዝብ ፡ ኹሉ ፡ ጠፍተዋልና ፥ ብርም ፡ የተሸከሙ ፡ ኹሉ ፡
ተቈርጠዋልና ፥ አልቅሱ ።

12 ፤ በዚያም ፡ ዘመን ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ በመብራት ፡ እመረምራለኹ ፤ በአተላቸውም ፡ ላይ ፡
የሚቀመጡትን ፥ በልባቸውም ፦ እግዚአብሔር ፡ መልካምን ፡ አያደርግም ፥ ክፉም ፡ አያደርግም ፡ የሚሉትን ፡ ሰዎች ፡
እቀጣለኹ ።

13 ፤ ብልጥግናቸውም ፡ ለምርኮ ፡ ይኾናል ፥ ቤቶቻቸውም ፡ ይፈርሳሉ ፤ ቤቶችንም ፡ ይሠራሉ ፥ ነገር ፡
ግን ፥ አይቀመጡባቸውም ፤ ወይንንም ፡ ይተክላሉ ፥ የወይን ፡ ጠጁን ፡ ግን ፡ አይጠጡም ።

14 ፤ ታላቁ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቀን ፡ ቀርቧል ፤ የእግዚአብሔር ፡ ቀን ፡ ድምፅ ፡ ቀርቧል ፡ እጅግም ፡ ፈጥኗል ፤ ኀያሉም ፡
በዚያ ፡ በመራራ ፡ ልቅሶ ፡ ይጮኻል ።

15 ፤ ያ ፡ ቀን ፡ የመዓት ፡ ቀን ፡ የመከራና ፡ የጭንቀት ፡ ቀን ፥ የመፍረስና ፡ የመጥፋት ፡ ቀን ፥ የጨለማና ፡ የጭጋግ ፡
ቀን ፥ የደመናና ፡ የድቅድቅ ፡ ጨለማ ፡ ቀን ፥

16 ፤ በተመሸጉ ፡ ከተማዎችና ፡ በረዘሙ ፡ ግንቦች ፡ ላይ ፡ የመለከትና ፡ የሰልፍ ፡ ጩኸት ፡ ቀን ፡ ነው ።

271 ዕብ. ፥ ጸፋንያሁ ፡ (ጸፈነ ፡ እግዚአ • ጌታ ፡ ሰወረ ፥ ጨፈነ) ።

17 ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ላይ ፡ ኀጢአት ፡ ሠርተዋልና ፥ እንደ ፡ ዕውር ፡ እስኪኼዱ ፡ ድረስ ፡ ሰዎችን ፡
አስጨንቃለኹ ፤ ደማቸውም ፡ እንደ ፡ ትቢያ ፥ ሥጋቸውም ፡ እንደ ፡ ጕድፍ ፡ ይፈሳል ።

18 ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ቍጣ ፡ ቀን ፡ ብራቸውና ፡ ወርቃቸው ፡ ሊያድናቸው ፡ አይችልም ፤ ርሱም ፡ በምድር ፡
የሚኖሩትን ፡ ኹሉ ፡ ፈጥኖ ፡ ይጨርሳቸዋልና ፥ ምድር ፡ ኹሉ ፡ በቅንአቱ ፡ እሳት ፡ ትበላለች ።

ትንቢተ ፡ ሶፎንያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 2 ።

ምዕራፍ ፡ 2 ።

1 ፤ 2 ፤ እናንተ ፡ ዕፍረት ፡ የሌላችኹ ፡ ሕዝብ ፡ ሆይ ፥ ትእዛዝ ፡ ሳይወጣ ፥ ቀኑም ፡ እንደ ፡ ገለባ ፡
ሳያልፍ ፥ የእግዚአብሔርም ፡ ቍጣ ፡ ትኵሳት ፡ ሳይመጣባችኹ ፥ የእግዚአብሔርም ፡ ቍጣ ፡ ቀን ፡ ሳይደርስባችኹ ፡
ተሰብሰቡ ፥ ተከማቹም ።

3 ፤ እናንተ ፡ ፍርዱን ፡ የጠበቃችኹ ፡ የምድር ፡ ትሑታን ፡ ኹሉ ፥ እግዚአብሔርን ፡ ፈልጉ ፤ ጽድቅንም ፡
ፈልጉ ፥ ትሕትናንም ፡ ፈልጉ ፤ ምናልባት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ ቀን ፡ ትሰወሩ ፡ ይኾናል ።

4 ፤ ጋዛ ፡ ትበረበራለች ፥ አስቀሎናም ፡ ባድማ ፡ ትኾናለች ፤ አዞጦንንም ፡ በቀትር ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡
ያሳድዷታል ፥ ዐቃሮንም ፡ ትነቀላለች ።

5 ፤ በባሕር ፡ ዳር ፡ ለሚኖሩ ፡ ለከሊታውያን ፡ ሕዝብ ፡ ወዮላቸው! የፍልስጥኤማውያን ፡ ምድር ፡ ከነዓን ፡
ሆይ ፥ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ባንተ ፡ ላይ ፡ ነው ፥ የሚቀመጥብኽም ፡ ሰው ፡ እንዳይኖር ፡ አጠፋኻለኹ ።

6 ፤ ቀርጤስም ፡ የእረኞች ፡ መኖሪያና ፡ የመንጋዎች ፡ በረት ፡ ይኾናል ።

7 ፤ የባሕሩም ፡ ዳር ፡ ለይሁዳ ፡ ቤት ፡ ቅሬታ ፡ ይኾናል ፥ በዚያም ፡ ይሰማራሉ ፤ አምላካቸው ፡ እግዚአብሔር ፡
ይጐበኛቸዋልና ፥ ምርኳቸውንም ፡ ይመልሳልና ፥ በአስቀሎና ፡ ቤቶች ፡ ውስጥ ፡ ማታ ፡ ይተኛሉ ።

8 ፤ በሕዝቤም ፡ ላይ ፡ ያላገጡባትን ፥ በድንበራቸውም ፡ ላይ ፡ እየታበዩ ፡ የተናገሩባትን ፡ የሞዐብን ፡ ማላገጥና ፡
የዐሞንን ፡ ልጆች ፡ ስድብ ፡ ሰምቻለኹ ።

9 ፤ ስለዚህ ፥ የእስራኤል ፡ አምላክ ፣ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ እኔ ፡ ሕያው ፡ ነኝና ፡ በርግጥ ፡
ሞዐብ ፡ እንደ ፡ ሰዶም ፥ የዐሞንም ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ ገሞራ ፥ የሳማ ፡ ስፍራና ፡ የጨው ፡ ጕድጓድ ፡ ለዘለዓለምም ፡
ምድረ ፡ በዳ ፡ ኾነው ፡ ይኖራሉ ፤ የሕዝቤም ፡ ቅሬታ ፡ ይበዘብዛቸዋል ፥ ከወገኔም ፡ የተረፉት ፡ ይወርሷቸዋል ።

10 ፤ በሰራዊት ፡ ጌታ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ሕዝብ ፡ ላይ ፡ አላግጠዋልና ፥ እየታበዩም ፡ ተናግረዋልና ፥ ይህ ፡ ስለ ፡
ትዕቢታቸው ፡ ያገኛቸዋል ።

11 ፤ እግዚአብሔር ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ የተፈራ ፡ ይኾናል ፥ የምድርንም ፡ አማልክት ፡ ኹሉ ፡ ያከሳቸዋል ፤ በአሕዛብም ፡
ደሴቶች ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ኹሉ ፡ በስፍራቸው ፡ ኾነው ፡ ለርሱ ፡ ይሰግዳሉ ።

12 ፤ እናንተም ፡ ኢትዮጵያውያን ፡ ደግሞ ፥ በሰይፌ ፡ ትገደላላችኹ ።

13 ፤ ርሱም ፡ በሰሜን ፡ ላይ ፡ እጁን ፡ ይዘረጋል ፥ አሶርንም ፡ ያጠፋል ፤ ነነዌንም ፡ ባድማ ፥ እንደ ፡ በረሓም ፡ ደረቅ ፡
ያደርጋታል ።

14 ፤ መንጋዎችም ፡ የምድርም ፡ አራዊት ፡ ኹሉ ፡ በውስጧ ፡ ይመሰጋሉ ፤ ይብራና ፡ ጃርት ፡ በዐምዶቿ ፡ መካከል ፡
ያድራሉ ፤ ድምፃቸው ፡ በመስኮቶቿ ፡ ይጮኻል ፤ የዝግባም ፡ ዕንጨት ፡ ሥራ ፡ ይገለጣልና ፥ በመድረኮቿ ፡ ላይ ፡ ጥፋት ፡
ይኾናል ።

15 ፤ ተዘልላ ፡ የተቀመጠች ፥ በልቧም ፦ እኔ ፡ ነኝ ፥ ከእኔም ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ የለም ፡ ያለች ፡ ደስተኛዪቱ ፡ ከተማ ፡
ይህች ፡ ናት ፤ አራዊት ፡ የሚመሰጉባት ፡ ባድማ ፡ እንዴት ፡ ኾነች! በርሷ ፡ በኩል ፡ የሚያልፈው ፡ ኹሉ ፡ እጁን ፡
እያወዛወዘ ፡ ያፏጫል ።

ትንቢተ ፡ ሶፎንያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 3 ።

ምዕራፍ ፡ 3 ።

1 ፤ ለዐመፀኛዪቱና ፡ ለረከሰች ፡ ለአስጨናቂዪቱም ፡ ከተማ ፡ ወዮላት!

2 ፤ ድምፅን ፡ አልሰማችም ፥ ተግሣጽንም ፡ አልተቀበለችም ፤ በእግዚአብሔርም ፡ አልታመነችም ፥ ወደ ፡ አምላኳም ፡
አልቀረበችም ።

3 ፤ በውስጧ ፡ ያሉ ፡ አለቃዎቿ ፡ እንደሚያገሡ ፡ አንበሳዎች ፡ ናቸው ፤ ፈራጆቿም ፡ እስከ ፡ ነገ ፡ ድረስ ፡ ምንም ፡
እንደማያስቀሩ ፡ እንደ ፡ ማታ ፡ ተኵላዎች ፡ ናቸው ።

4 ፤ ነቢያቷ ፡ ቀሌታሞችና ፡ ተንኰለኛዎች ፡ ሰዎች ፡ ናቸው ፤ ካህናቷም ፡ መቅደሱን ፡ አርክሰዋል ፥ በሕግም ፡ ላይ ፡ ግፍ ፡
ሠርተዋል ።

5 ፤ እግዚአብሔር ፡ በውስጧ ፡ ጻድቅ ፡ ነው ፤ ክፋትን ፡ አያደርግም ፤ ፍርዱን ፡ በየማለዳው ፡ ወደ ፡ ብርሃን ፡
ያወጣል ፥ ሳያወጣውም ፡ አይቀርም ፤ ዐመፀኛው ፡ ግን ፡ ዕፍረትን ፡ አያውቅም ።

6 ፤ አሕዛብን ፡ አጥፍቻለኹ ፤ ግንቦቻቸው ፡ ኹሉ ፡ ፈርሰዋል ፤ መንገዳቸውን ፡ ማንም ፡ እንዳያልፍባት ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡
አድርጌያለኹ ፥ ከተማዎቻቸውም ፡ ማንም ፡ እንዳይኖርባቸው ፥ አንድስ ፡ እንኳ ፡ እንዳይቀመጥባቸው ፡ ፈርሰዋል ።

7 ፤ እኔም ፡— ይፈሩኛል ፥ ተግሣጽንም ፡ ይቀበላሉ ፤ ካዘዝኍትም ፡ ኹሉ ፡ ከዐይኗ ፡ ምንም ፡ አይጠፋም ፡ ብዬ ፡
ነበር ፤ እነርሱ ፡ ግን ፡ በማለዳ ፡ ተነሥተው ፡ ድርጊታቸውን ፡ ኹሉ ፡ አረከሱ ።

8 ፤ መዓቴንና ፡ የቍጣዬን ፡ ትኵሳት ፡ ኹሉ ፡ አፈስባቸው ፡ ዘንድ ፡ ፍርዴ ፡ አሕዛብን ፡ ለመሰብሰብ ፥ መንግሥታትንም ፡
ለማከማቸት ፡ ነውና ፥ ምድርም ፡ ኹሉ ፡ በቅንአቴ ፡ እሳት ፡ ትበላለችና ፡ ስለዚህ ፡ ለመበዝበዝ ፡ እስከምነሣበት ፡ ቀን ፡
ድረስ ፡ ጠብቁኝ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

9 ፤ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ አሕዛብ ፡ ኹሉ ፡ አንድ ፡ ኾነው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያገለግሉት ፡ ዘንድ ፡ ስሙን ፡ እንዲጠሩ ፡
ንጹሓን ፡ ልሳን ፡ እመልስላቸዋለኹ ።

10 ፤ ከኢትዮጵያ ፡ ወንዞች ፡ ማዶ ፡ የሚማልዱኝ ፥ የተበተኑት ፡ ሴቶች ፡ ልጆቼ ፥ ቍርባኔን ፡ ያመጡልኛል ።

11 ፤ በዚያን ፡ ጊዜ ፡ እየታበዩ ፡ የሚፎክሩትን ፡ ከመካከልሽ ፡ አወጣለኹና ፥ አንቺም ፡ በቅዱስ ፡ ተራራዬ ፡ ዳግመኛ ፡
አትኰሪምና ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ተላልፈሽ ፡ በሠራሽው ፡ ሥራ ፡ ኹሉ ፡ አትፍሪም ።

12 ፤ በመካከልሽም ፡ የዋህና ፡ ትሑት ፡ ሕዝብን ፡ አስቀራለኹ ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ስም ፡ ይታመናሉ ።

13 ፤ የእስራኤል ፡ ቅሬታ ፡ ኀጢአትን ፡ አይሠሩም ፥ ሐሰትንም ፡ አይናገሩም ፥ በአፋቸውም ፡ ውስጥ ፡ ተንኰለኛ ፡ ምላስ ፡
አይገኝም ፤ እነርሱም ፡ ይሰማራሉ ፥ ይመሰገማል ፥ የሚያስፈራቸውም ፡ የለም ።

14 ፤ የጽዮን ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ ዘምሪ ፤ እስራኤል ፡ ሆይ ፥ እልል ፡ በል ፤ የኢየሩሳሌም ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ በፍጹም ፡ ልብሽ ፡
ሐሤት ፡ አድርጊ ፡ ደስም ፡ ይበልሽ ።

15 ፤ እግዚአብሔር ፡ ፍርድሽን ፡ አስወግዷል ፥ ጠላትሽንም ፡ ጥሏል ፤ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ እግዚአብሔር ፡ በመካከልሽ ፡
አለ ፥ ከእንግዲህም ፡ ወዲህ ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡ አታዩም ።

16 ፤ በዚያን ፡ ቀን ፡ ለኢየሩሳሌም ፡— ጽዮን ፡ ሆይ ፥ አትፍሪ ፥ እጆችሽም ፡ አይዛሉ ።

17 ፤ አምላክሽ ፡ እግዚአብሔር ፡ በመካከልሽ ፡ ታዳጊ ፡ ኀያል ፡ ነው ፤ በደስታ ፡ ባንቺ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፥ በፍቅሩም ፡
ያርፋል ፥ በእልልታም ፡ ባንቺ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፡ ይባላል ።

18 ፤ ከጉባኤው ፡ ርቀው ፡ የሚያዝኑትን ፥ ከአንቺም ፡ የኾኑትን ፡ እሰበስባለኹ ፤ ስድብ ፡ እንደ ፡ ሸክም ፡ ከብዶባቸው ፡
ነበር ።

19 ፤ በዚያ ፡ ዘመን ፥ እንሆ ፥ ባስጨነቁሽ ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፡ አደርግባቸዋለኹ ፤ ዐንካሳዪቱንም ፡
አድናለኹ ፥ የተጣለችውንም ፡ እሰበስባታለኹ ፤ ባፈሩባትም ፡ ምድር ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፡ ለምስጋናና ፡ ለክበረ ፡ ስም ፡
አደርጋቸዋለኹ ።

20 ፤ በዚያ ፡ ዘመን ፡ አስገባችኋለኹ ፥ በዚያም ፡ ዘመን ፡ እሰበስባችኋለኹ ፤ ምርኳችኹንም ፡ በዐይናችኹ ፡ ፊት ፡
በመለስኹ ፡ ጊዜ ፡ በምድር ፡ አሕዛብ ፡ ኹሉ ፡ መካከል ፡ ለክበረ ፡ ስምና ፡ ለምስጋና ፡ አደርጋችኋለኹ ፥ ይላል ፡

# ትንቢተ ፡ ሐጌ ።

(ክለሳ.1.20020507)

________________ትንቢ.ተ ፡ ሐጌ ፥ ምዕራፍ ፡ 1 ። ________________

ምዕራፍ ፡ 1 ።

1 ፤ በንጉሡ ፡ በዳርዮስ ፡ በኹለተኛው ፡ ዓመት ፡ በስድስተኛው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በመዠመሪያው ፡ ቀን ፡
የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ በነቢዩ ፡ በሐጌ ፡ እጅ ፡ ወደይሁዳ ፡ አለቃ ፡ ወደሰላትያል ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ዘሩባቤል ፥ ወደ ፡
ታላቁም ፡ ካህን ፡ ወደኢዮሴዴቅ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ኢያሱ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፦

2 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፦ ይህ ፡ ሕዝብ ፦ ዘመኑ ፡ አልደረሰም ፥ የእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ የሚሠራበት ፡
ዘመን ፡ አልደረሰም ፡ ይላል ፡ ብሎ ፡ ተናገረ ።

3 ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ በነቢዩ ፡ በሐጌ ፡ እጅ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፦

4 ፤ በእውኑ ፡ ይህ ፡ ቤት ፡ ፈርሶ ፡ ሳለ ፡ እናንተ ፡ ራሳችኹ ፡ በተሸለሙ ፡ ቤቶቻችኹ ፡ ለመኖር ፡ ጊዜው ፡ ነውን ፧

5 ፤ አኹንም ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ልባችኹን ፡ በመንገዳችኹ ፡ ላይ ፡ አድርጉ ።

6 ፤ ብዙ ፡ ዘራችኹ ፥ ጥቂትም ፡ አገባችኹ ፤ በላችኹ ፥ ነገር ፡ ግን ፥ አልጠገባችኹም ፤ ጠጣችኹ ፥ ነገር ፡
ግን ፥ አልረካችኹም ፤ ለበሳችኹ ፥ ነገር ፡ ግን ፥ አልሞቃችኹም ፤ ደመ ፡ ወዙን ፡ የተቀበለ ፡ ሰው ፡ በቀዳዳ ፡ ከረጢት ፡
ያደርገው ፡ ዘንድ ፡ ደመ ፡ ወዙን ፡ ተቀበለ ።

7 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ልባችኹን ፡ በመንገዳችኹ ፡ ላይ ፡ አድርጉ ።

8 ፤ ወደ ፡ ተራራው ፡ ውጡ ፥ ዕንጨትንም ፡ አምጡ ፥ ቤቱንም ፡ ሥሩ ፤ እኔም ፡ በርሱ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፥ እኔም ፡
እመሰገናለኹ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

9 ፤ እናንተ ፡ ብዙ ፡ ነገርን ፡ ተስፋ ፡ አደረጋችኹ ፥ እንሆም ፥ ጥቂት ፡ ኾነ ፤ ወደ ፡ ቤትም ፡ ባገባችኹት ፡ ጊዜ ፡ እፍ ፡
አልኹበት ፦ ይህ ፡ ስለ ፡ ምንድር ፡ ነው ፧ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፦ እናንተ ፡ ኹሉ ፡ ወደ ፡
እየቤታችኹ ፡ እየሮጣችኹ ፡ የእኔ ፡ ቤት ፡ ፈርሶ ፡ ስለ ፡ ተቀመጠ ፡ ነው ።

10 ፤ ስለዚህ ፥ ሰማያት ፡ በላያችኹ ፡ ጠልን ፡ ከልክለዋል ፥ ምድሪቱም ፡ ፍሬዋን ፡ ከልክላለች ።

11 ፤ እኔም ፡ በምድርና ፡ በተራራዎች ፥ በእኽልና ፡ በወይንም ፥ በዘይትና ፡ ምድርም ፡ በምታበቅለው ፡ ላይ ፥ በሰዎችና ፡
በእንስሳዎችም ፡ ላይ ፥ እጅም ፡ በሚደክምበት ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፡ ድርቅን ፡ ጠርቻለኹ ።

12 ፤ የሰላትያልም ፡ ልጅ ፡ ዘሩባቤል ፥ ታላቁም ፡ ካህን ፡ የኢዮሴዴቅ ፡ ልጅ ፡ ኢያሱ ፥ የቀሩትም ፡ ሕዝብ ፡ ኹሉ ፡
የአምላካቸውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ድምፅ ፡ የነቢዩንም ፡ የሐጌን ፡ ቃል ፥ አምላካቸው ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ላከው ፡
ኹሉ ፡ ሰሙ ፤ ሕዝቡም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ፈሩ ።

13 ፤ የእግዚአብሔርም ፡ መልእክተኛ ፡ ሐጌ ፡ በእግዚአብሔር ፡ መልእክት ፡ ሕዝቡን ፦ እኔ ፡ ከእናንተ ፡ ጋራ ፡
ነኝ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፡ ብሎ ፡ ተናገረ ።

14 ፤ 15 ፤ እግዚአብሔርም ፡ የይሁዳን ፡ አለቃ ፡ የሰላትያልን ፡ ልጅ ፡ የዘሩባቤልን ፡ መንፈስ ፥ የታላቁንም ፡ ካህን ፡
የኢዮሴዴቅን ፡ ልጅ ፡ የኢያሱን ፡ መንፈስ ፥ የቀሩትንም ፡ ሕዝብ ፡ ኹሉ ፡ መንፈስ ፡ አስነሣ ፤ በንጉሡም ፡ በዳርዮስ ፡
በኹለተኛው ፡ ዓመት ፡ በስድስተኛው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በኻያ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ መጡ ፥ የአምላካቸውንም ፡
የሰራዊትን ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤት ፡ ሠሩ ።

________________ትንቢ.ተ ፡ ሐጌ ፥ ምዕራፍ ፡ 2 ። ________________

ምዕራፍ ፡ 2 ።

1 ፤ በሰባተኛው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በኻያ ፡ አንደኛው ፡ ቀን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ በነቢዩ ፡ በሐጌ ፡ እጅ ፡ እንዲህ ፡

ሲል ፡ መጣ ፡—

2 ፤ ለይሁዳ ፡ አለቃ ፡ ለሰላትያል ፡ ልጅ ፡ ለዘሩባቤል ፥ ለታላቁም ፡ ካህን ፡ ለኢዮሴዴቅ ፡ ልጅ ፡ ለኢያሱ ፥ ለቀሩትም ፡ ሕዝብ ፡ እንዲህ ፡ ስትል ፡ ተናገር ።

3 ፤ በቀድሞ ፡ ክብሩ ፡ ሳለ ፡ ይህን ፡ ቤት ፡ ያየ ፡ በእናንተ ፡ መካከል ፡ የቀረ ፡ ማን ፡ ነው ፧ ዛሬስ ፡ እንዴት ፡ ኾኖ ፡ አያችኹት ፧ በዐይናችኹ ፡ እንደ ፡ ምናምን ፡ አይደለምን ፧

4 ፤ አኹን ፡ ግን ፥ ዘሩባቤል ፡ ሆይ ፥ በርታ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ ታላቁም ፡ ካህን ፡ የኢዮሴዴቅ ፡ ልጅ ፡ ኢያሱ ፡ ሆይ ፥ በርታ ፥ እናንተም ፡ የአገሩ ፡ ሕዝብ ፡ ሆይ ፥ በርቱና ፡ ሥሩ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ እኔ ፡ ከእናንተ ፡ ጋራ ፡ ነኝና ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

5 ፤ መንፈሴም ፡ በመካከላችኹ ፡ ይኖራልና ፥ አትፍሩ ።

6 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፡— ገና ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ በቅርብ ፡ ዘመን ፡ እኔ ፡ ሰማያትንና ፡ ምድርን ፡ ባሕርንና ፡ የብስንም ፡ አናውጣለኹ ፤

7 ፤ አሕዛብን ፡ ዅሉ ፡ አናውጣለኹ ፥ በአሕዛብ ፡ ዅሉ ፡ የተመረጠውም ፡ ዕቃ ፡ ይመጣል ፤ ይህንም ፡ ቤት ፡ በክብር ፡ እሞላዋለኹ ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

8 ፤ ብሩ ፡ የእኔ ፡ ነው ፥ ወርቁም ፡ የእኔ ፡ ነው ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

9 ፤ ከፊተኛው ፡ ይልቅ ፡ የዚህ ፡ የኋለተኛው ፡ ቤት ፡ ክብር ፡ ይበልጣል ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ በዚህም ፡ ስፍራ ፡ ሰላምን ፡ እሰጣለኹ ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

10 ፤ በዳርዮስም ፡ በኹለተኛው ፡ ዓመት ፡ በዘጠነኛው ፡ ወር ፡ በኻያ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ በነቢዩ ፡ በሐጌ ፡ እጅ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡—

11 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፡— ካህናቱን ፡ ስለ ፡ ሕጉ ፡ ጠይቅ ፤

12 ፤ አንድ ፡ ሰው ፡ የተቀደሰ ፡ ሥጋ ፡ በልብሱ ፡ ዘርፍ ፡ ቢይዝ ፥ በዘርፉም ፡ እንጀራ ፡ ወይም ፡ ወጥ ፥ ወይም ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፥ ወይም ፡ ዘይት ፥ ወይም ፡ ማናቸውም ፡ መብል ፡ ቢነካ ፡ ያ ፡ የተነካው ፡ በእውኑ ፡ ይቀደሳልን ፧ ብለኽ ፡ ካህናቱን ፡ ጠይቃቸው ፤ ካህናቱም ፡— አይኾንም ፡ ብለው ፡ መለሱ ።

13 ፤ ሐጌም ፡— በሬሳ ፡ የረከሰ ፡ ሰው ፡ ከነዚህ ፡ አንዱን ፡ ቢነካ ፡ ያ ፡ የተነካው ፡ በእውኑ ፡ ይረክሳልን ፧ አለ ። ካህናቱም ፡— አዎን ፡ ይረክሳል ፡ ብለው ፡ መለሱ ።

14 ፤ ሐጌም ፡ መልሶ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡— ይህ ፡ ሕዝብና ፡ ይህ ፡ ወገን ፡ በፊቴ ፡ እንዲሁ ፡ ነው ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ የእጃቸውም ፡ ሥራ ፡ ዅሉ ፡ እንዲሁ ፡ ነው ፤ በዚያም ፡ ያቀረቡት ፡ ነገር ፡ ርኩስ ፡ ነው ።

15 ፤ አኹንም ፡ ድንጋይ ፡ በድንጋይ ፡ ላይ ፡ በእግዚአብሔር ፡ መቅደስ ፡ ሳይነባበር ፥ ከዛሬ ፡ ዠምራችኹ ፡ ወዳለፈው ፡ ዘመን ፡ ልብ ፡ አድርጉ ።

16 ፤ በዚያን ፡ ዘመን ፡ ዅሉ ፡ ሰው ፡ ኻያ ፡ መስፈሪያ ፡ ወዳለበት ፡ ምርት ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፥ የተገኘው ፡ ዐሥር ፡ መስፈሪያ ፡ ብቻ ፡ ነው ፤ ዐምሳ ፡ ማድጋም ፡ ይቀዳ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ መጥመቂያው ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፥ የተገኘው ፡ ኻያ ፡ ብቻ ፡ ነው ።

17 ፤ በእጃችኹ ፡ ሥራ ፡ ዅሉ ፡ ላይ ፡ በዋግና ፡ በዐረማሞ ፡ በበረዶም ፡ መታኋችኹ ፤ እናንተ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ አልተመለሳችኹም ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

18 ፤ ከዛሬው ፡ ከዘጠነኛው ፡ ወር ፡ ከኻያ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ ዠምራችኹ ፡ የሚመጣውን ፡ ዘመን ፡ ልብ ፡ አድርጉ ፤ የእግዚአብሔር ፡ መቅደስ ፡ መሠረት ፡ ከተተከለበት ፡ ቀን ፡ ዠምሮ ፡ ልብ ፡ አድርጉ ።

19 ፤ ዘር ፡ በጐተራ ፡ ገና ፡ ይኖራልን ፧ ወይንና ፡ በለስ ፡ ሮማንና ፡ ወይራ ፡ አላፈሩም ፤ ከዚች ፡ ቀን ፡ ዠምሬ ፡ እባርካችኋለኹ ።

20 ፤ በወሩ ፡ በኻያ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ኹለተኛ ፡ ወደ ፡ ሐጌ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፡—

21 ፤ ለይሁዳ ፡ አለቃ ፡ ለዘሩባቤል ፡ ተናገር ፡ እንዲህም ፡ በል ፦ ሰማያትንና ፡ ምድርን ፡ አናውጣለኹ ፤

22 ፤ የመንግሥታትንም ፡ ዙፋን ፡ እገለብጣለኹ ፥ የአሕዛብንም ፡ መንግሥታት ፡ ኀይል ፡ አጠፋለኹ ፤ ሠረገላዎችንና ፡
የሚቀመጡባቸውንም ፡ እገለብጣለኹ ፤ ፈረሶችና ፡ ፈረሰኞዎቻቸውም ፡ እያንዳንዳቸው ፡ በወንድማቸው ፡ ሰይፍ ፡
ይወድቃሉ ።

23 ፤ ባሪያዬ ፡ የሰላትያል ፡ ልጅ ፡ ዘሩባቤል ፡ ሆይ ፥ በዚያ ፡ ቀን ፡ እወስድኻለኹ ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔር ፤ እኔ ፡ መርጬኻለኹና ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፥ እንደ ፡ ቀለበት ፡ ማተሚያ ፡ አደርግኻለኹ ፥ ይላል ፡
የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፨

# ትንቢተ ፡ ዘካርያስ ።

(ክለሳ.1.20020507)

## ትንቢተ ፡ ዘካርያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 1 ።

ምዕራፍ ፡ 1 ።

1 ፤ በዳርዮስ ፡ በኹለተኛው ፡ ዓመት ፡ በስምንተኛው ፡ ወር ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደአዶ ፡ ልጅ ፡ ወደበራክዩ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ነቢዩ ፡ ወደ ፡ ዘካርያስ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፦

2 ፤ እግዚአብሔር ፡ በአባቶቻችኹ ፡ ላይ ፡ እጅግ ፡ ተቈጥቶ ፡ ነበር ።

3 ፤ ስለዚህ ፥ እንዲህ ፡ በላቸው ፦ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ወደ ፡ እኔ ፡ ተመለሱ ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፥ እኔም ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ እመለሳለኹ ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

4 ፤ የቀደሙት ፡ ነቢያት ፡ ለአባቶቻችኹ ፡ እንዲህ ፡ ብለው ፡ ሰብከዋል ፦ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ከክፉ ፡ መንገዳችኹና ፡ ከክፉ ፡ ሥራችኹ ፡ ተመለሱ ፤ እነርሱ ፡ ግን ፡ አልሰሙም ፥ እኔንም ፡ አላደመጡም ፤ እንደ ፡ እነርሱ ፡ አትኹኑ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

5 ፤ አባቶቻችኹ ፡ ወዴት ፡ ናቸው ፧ ነቢያትስ ፡ ለዘለዓለም ፡ በሕይወት ፡ ይኖራሉን ፧

6 ፤ ለባሪያዎቼስ ፡ ለነቢያት ፡ ያዘዝኋቸው ፡ ቃሎቼና ፡ ሥርዐቴ ፡ በአባቶቻችኹ ፡ ላይ ፡ አልደረሱምን ፧ እነርሱም ፡ ተመልሰው ፦ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ በመንገዳችንና ፡ በሥራችን ፡ መጠን ፡ ያደርግብን ፡ ዘንድ ፡ እንዳሰበ ፡ እንዲሁ ፡ አድርጎብናል ፡ አሉ ።

7 ፤ በዳርዮስ ፡ በኹለተኛው ፡ ዓመት ፡ ሳባጥ ፡ በሚባል ፡ በዐሥራ ፡ አንደኛው ፡ ወር ፡ በኻያ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደአዶ ፡ ልጅ ፡ ወደበራክዩ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ነቢዩ ፡ ወደ ፡ ዘካርያስ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፦

8 ፤ እንሆም ፥ አንድ ፡ ሰው ፡ በመጋላ ፡ ፈረስ ፡ ተቀምጦ ፡ በሌሊት ፡ አየኹ ፥ ርሱም ፡ በሸለቆው ፡ ውስጥ ፡ ባሉ ፡ በባርሰነት ፡ ዛፎች ፡ መካከል ፡ ቆሞ ፡ ነበር ፤ በስተ ኋላውም ፡ መጋላና ፡ ሐመር ፡ ዐምባላይም ፡ ፈረሶች ፡ ነበሩ ።

9 ፤ እኔም ፦ ጌታዬ ፡ ሆይ ፥ እነዚህ ፡ ምንድር ፡ ናቸው ፧ አልኹ ። ከእኔም ፡ ጋራ ፡ ይነጋገር ፡ የነበረው ፡ መልአክ ፦ እነዚህ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ኾኑ ፡ አሳይኻለኹ ፡ አለኝ ።

10 ፤ በባርሰነት ፡ ዛፎች ፡ መካከልም ፡ ቆሞ ፡ የነበረው ፡ ሰው ፦ እነዚህ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ይመላለሱ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ የላካቸው ፡ ናቸው ፡ ብሎ ፡ መለሰ ።

11 ፤ በባርሰነት ፡ ዛፎች ፡ መካከልም ፡ ቆሞ ፡ የነበረውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መልአክ ፦ በምድር ፡ ላይ ፡ ተመላለስን ፥ እንሆም ፥ ምድር ፡ ኹሉ ፡ ዝም ፡ ብላ ፡ ዐርፋ ፡ ተቀምጣለች ፡ ብለው ፡ መለሱለት ።

12 ፤ የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ መልሶ ፦ አቤቱ ፥ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ ሆይ ፥ እነዚህ ፡ ሰባ ፡ ዓመት ፡ የተቈጣኻቸውን ፡ ኢየሩሳሌምንና ፡ የይሁዳን ፡ ከተማዎች ፡ የማትምራቸው ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ነው ፧ አለ ።

13 ፤ እግዚአብሔርም ፡ መልሶ ፡ ከእኔ ፡ ጋራ ፡ ይነጋገር ፡ ለነበረው ፡ መልአክ ፡ በመልካምና ፡ በሚያጽናና ፡ ቃል ፡ ተናገረው ።

14 ፤ ስለዚህም ፡ ከእኔ ፡ ጋራ ፡ ይነጋገር ፡ የነበረው ፡ መልአክ ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፦ ስበክ ፡ እንዲህም ፡ በል ፦ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ እኔ ፡ በታላቅ ፡ ቅንአት ፡ በኢየሩሳሌምና ፡ በጽዮን ፡ ቀንቻለኹ ።

15 ፤ እኔ ፡ ጥቂት ፡ ብቻ ፡ ተቈጥቼ ፡ ሳለኹ ፡ እነርሱ ፡ ክፉትን ፡ ስላገዙት ፥ ባልተቸገሩት ፡ አሕዛብ ፡ ላይ ፡ እጅግ ፡ ተቈጥቻለኹ ።

16 ፤ ስለዚህ ፥ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ በምሕረት ፡ ተመልሻለኹ ፤ ቤቴ ፡ ይሠራባታል ፤ በኢየሩሳሌምም ፡ ላይ ፡ ገመድ ፡ ይዘረጋበታል ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

17 ፤ ደግሞም ፡ እንዲህ ፡ ስትል ፡ ስበክ ፦ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ከተማዎቼ ፡ ደግሞ ፡
በበጎ ፡ ነገር ፡ ይረካሉ ፤ እግዚአብሔርም ፡ ደግሞ ፡ ጽዮንን ፡ ያጽናናል ፥ ኢየሩሳሌምንም ፡ ደግሞ ፡ ይመርጣል ።

18 ፤ ዐይኖቼንም ፡ አንሥቼ ፥ እንሆ ፥ አራት ፡ ቀንዶች ፡ አየኹ ።

19 ፤ ከእኔም ፡ ጋራ ፡ ይነጋገር ፡ የነበረውን ፡ መልአክ ፦ እነዚህ ፡ ምንድር ፡ ናቸው ፧ አልኹት ። ርሱም ፦ እነዚህ ፡
ይሁዳንና ፡ እስራኤልን ፡ ኢየሩሳሌምንም ፡ የበተኑ ፡ ቀንዶች ፡ ናቸው ፡ ብሎ ፡ መለሰልኝ ።

20 ፤ እግዚአብሔርም ፡ አራት ፡ ጠራቢዎች ፡ አሳየኝ ።

21 ፤ እኔም ፦ እነዚህ ፡ የመጡት ፡ ምን ፡ ሊሠሩ ፡ ነው ፧ አልኹ ። ርሱም ፦ አንድ ፡ ሰው ፡ ራሱን ፡ እስከማያነሣ ፡
ድረስ ፡ እነዚህ ፡ ቀንዶች ፡ ይሁዳን ፡ የበተኑ ፡ ናቸው ፤ እነዚህ ፡ ግን ፡ ሊያስፈራሯቸው ፥ የይሁዳንም ፡ አገር ፡ ይበትኑ ፡
ዘንድ ፡ ቀንዳቸውን ፡ ያነሡትን ፡ የአሕዛብን ፡ ቀንዶች ፡ ሊጥሉ ፡ መጥተዋል ፡ ብሎ ፡ ተናገረ ።

_________________ትንቢተ ፡ ዘካርያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 2 ። _________________

ምዕራፍ ፡ 2 ።

1 ፤ ዐይኖቼንም ፡ አነሣኹ ፤ እንሆም ፥ በእጁ ፡ የመለኪያ ፡ ገመድ ፡ የያዘ ፡ አንድ ፡ ሰውን ፡ አየኹ ።

2 ፤ እኔም ፦ አንተ ፡ ወዴት ፡ ትኼዳለኽ ፧ አልኹ ። ርሱም ፦ የኢየሩሳሌምን ፡ ወርድና ፡ ርዝመት ፡ ስንት ፡ መኾኑን ፡
ሰፍሬ ፡ አይ ፡ ዘንድ ፡ እኼዳለኹ ፡ አለኝ ።

3 ፤ እንሆም ፥ ከእኔ ፡ ጋራ ፡ ይነጋገር ፡ የነበረው ፡ መልአክ ፡ ወጣ ፥ ሌላም ፡ መልአክ ፡ ሊገናኘው ፡ ወጣ ፥

4 ፤ እንዲህም ፡ አለው ፦ ሩጥ ፥ ይህንም ፡ ጕልማሳ ፡ እንዲህ ፡ በለው ፦ ኢየሩሳሌም ፡ በውስጧ ፡ ካሉት ፡ ሰዎችና ፡
እንስሳዎች ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ ቅጥር ፡ እንደሌላቸው ፡ መንደሮች ፡ ኾና ፡ ትኖራለች ።

5 ፤ እኔ ፡ በዙሪያዋ ፡ የእሳት ፡ ቅጥር ፡ እኾንላታለኹ ፥ በውስጧም ፡ ክብርን ፡ እኾናለኹ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

6 ፤ እናንተ ፡ ሆይ ፥ ከሰሜን ፡ ምድር ፡ ሽሹ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ እንደ ፡ አራቱ ፡ የሰማይ ፡ ነፋሳት ፡
በትኛችኋለኹና ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

7 ፤ አንቺ ፡ ከባቢሎን ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ጋራ ፡ የምትኖሪ ፡ ጽዮን ፡ ሆይ ፥ ኰብልዪ ።

8 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፦ ከክብሩ ፡ በኋላ ፡ ወደበዘበዟችኹ ፡ አሕዛብ ፡
ልኮኛል ፤ የሚነካችኹ ፡ የዐይኑን ፡ ብሌን ፡ የሚነካ ፡ ነውና ።

9 ፤ እንሆ ፥ እጄን ፡ በላያቸው ፡ አወዛውዛለኹ ፥ ተገዝተው ፡ ለነበሩት ፡ ብዝበዛ ፡ ይኾናሉ ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ላከኝ ፡ ታውቃላችኹ ።

10 ፤ የጽዮን ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ እንሆ ፥ መጥቼ ፡ በመካከልሽ ፡ እኖራለኹና ፡ ዘምሪ ፥ ደስም ፡ ይበልሽ ፥ ይላል ፡
እግዚአብሔር ።

11 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ ብዙ ፡ አሕዛብ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይጠጋሉ ፥ ሕዝብም ፡ ይኾኑኛል ፤ በመካከልሽም ፡
እኖራለኹ ፥ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ወደ ፡ አንቺ ፡ እንደ ፡ ላከኝ ፡ ታውቂያለሽ ።

12 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ይሁዳን ፡ ዕድል ፡ ፈንታው ፡ አድርጎ ፡ በተቀደሰችው ፡ ምድር ፡ ይወርሰዋል ፥ ኢየሩሳሌምንም ፡
ዳግመኛ ፡ ይመርጣል ።

13 ፤ እግዚአብሔር ፡ ከተቀደሰ ፡ ማደሪያው ፡ ነቅቷልና ፥ ሥጋ ፡ ለባሽ ፡ ኹሉ ፡ ሆይ ፥ በፊቱ ፡ ዝም ፡ በል ።

_________________ትንቢተ ፡ ዘካርያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 3 ። _________________

ምዕራፍ ፡ 3 ።

1 ፤ ርሱም ፡ ታላቁን ፡ ካህን ፡ ኢያሱን ፡ በእግዚአብሔር ፡ መልአክ ፡ ፊት ፡ ቆሞ ፡ አሳየኝ ፥ ሰይጣንም ፡ ይከሰው ፡ ዘንድ ፡
በስተቀኙ ፡ ቆሞ ፡ ነበር ።

2 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ሰይጣንን ፦ ሰይጣን ፡ ሆይ ፥ እግዚአብሔር ፡ ይገሥጽኽ ፤ ኢየሩሳሌምን ፡ የመረጠ ፡

እግዚአብሔር ፡ ይገሥጽኽ ፤ በእውኑ ፡ ይህ ፡ ከእሳት ፡ የተነጠቀ ፡ ትንታግ ፡ አይደለምን ፡ አለው ።

3 ፤ ኢያሱም ፡ እድፋም ፡ ልብስ ፡ ለብሶ ፡ በመልአኩ ፡ ፊት ፡ ቆሞ ፡ ነበር ። ርሱም ፡ መልሶ ፡ በፊቱ ፡
የቆሙትን ፦ እድፋሙን ፡ ልብስ ፡ ከርሱ ፡ ላይ ፡ አውልቁ ፡ አላቸው ። ርሱንም ፦ እንሆ ፥ አበሳኽን ፡ ከአንተ ፡
አርቄያለኹ ፥ ጥሩ ፡ ልብስም ፡ አለብስኻለኹ ፡ አለው ።

5 ፤ ደግሞ ፦ ንጹሕ ፡ ጥምጥም ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ አድርጉ ፡ አለ ። እነርሱም ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ንጹሕ ፡ ጥምጥም ፡
አደረጉ ፥ ልብስንም ፡ አለበሱት ፤ የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ በአጠገቡ ፡ ቆሞ ፡ ነበር ።

6 ፤ የእግዚአብሔርም ፡ መልአክ ፡ በኢያሱ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ አዳኘበት ።

7 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ በመንገዴ ፡ ብትኼድ ፡ ትእዛዜንም ፡ ብትጠብቅ ፥ በቤቴ ፡ ላይ ፡
ትፈርዳለኽ ፥ አደባባዮቼንም ፡ ትጠብቃለኽ ፥ በዚህም ፡ ከቆሙት ፡ ከነዚህ ፡ ጋራ ፡ መግባትን ፡ እሰጣለኹ ።

8 ፤ ታላቁ ፡ ካህን ፡ ኢያሱ ፡ ሆይ ፥ ስማ ፤ በፊትኽም ፡ የሚቀመጡት ፡ ባልንጀራዎችኽ ፡ ለምልክት ፡ የሚኾኑ ፡ ሰዎች ፡
ናቸውና ፥ ይስሙ ፤ እንሆ ፥ እኔ ፡ ባሪያዬን ፡ ቍጥቋጥ ፡ አወጣለኹ ።

9 ፤ በኢያሱ ፡ ፊት ፡ ያኖርኹት ፡ ድንጋይ ፥ እንሆ ፥ አለ ፤ በአንዱ ፡ ድንጋይ ፡ ላይ ፡ ሰባት ፡ ዐይኖች ፡
አሉ ፤ እንሆ ፥ ቅርጹን ፡ እቀርጻለኹ ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፥ የዚያችንም ፡ ምድር ፡ በደል ፡ ባንድ ፡
ቀን ፡ አስወግዳለኹ ።

10 ፤ በዚያ ፡ ቀን ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፥ እያንዳንዱ ፡ ከወይኑና ፡ ከበለሱ ፡ በታች ፡ ኾኖ ፡
ባልንጀራውን ፡ ይጠራል ።

## ትንቢተ ፡ ዘካርያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 4 ።

ምዕራፍ ፡ 4 ።

1 ፤ ከእኔም ፡ ጋራ ፡ ይነጋገር ፡ የነበረው ፡ መልአክ ፡ ተመልሶ ፡ ከእንቅልፉ ፡ እንደሚነቃ ፡ ሰው ፡ አነቃኝ ።

2 ፤ ርሱም ፦ የምታየው ፡ ምንድር ፡ ነው ፡ አለኝ ። እኔም ፦ እንሆ ፥ ኹለንተናው ፡ ወርቅ ፡ የኾነውን ፡ መቅረዝ ፡
አየኹ ፤ የዘይትም ፡ ማሰሮ ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ነበረ ፥ ሰባትም ፡ መብራቶች ፡ ነበሩበት ፤ በራሱም ፡ ላይ ፡ ለነበሩት ፡
መብራቶች ፡ ሰባት ፡ ቧንቧዎች ፡ ነበሯቸው ።

3 ፤ ኹለት ፡ የወይራ ፡ ዛፎች ፥ አንዱ ፡ በማሰሮው ፡ በስተቀኝ ፡ አንዱም ፡ በስተግራው ፡ ኾነው ፥ በአጠገቡ ፡ ነበሩ ፡
አልኹ ።

4 ፤ ከእኔ ፡ ጋራ ፡ ይነጋገር ፡ ለነበረውም ፡ መልአክ ፡ መልሼ ፦ ጌታዬ ፡ ሆይ ፥ እነዚህ ፡ ምንድር ፡ ናቸው ፡ አልኹት ።

5 ፤ ከእኔ ፡ ጋራ ፡ ይነጋገር ፡ የነበረውም ፡ መልአክ ፡ መልሶ ፦ እነዚህ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ኾኑ ፡
አታውቅምን ፡ አለኝ ። እኔም ፦ ጌታዬ ፡ ሆይ ፥ አላውቅም ፡ አልኹ ።

6 ፤ መልሶም ፦ ለዘሩባቤል ፡ የተባለው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ፦ በመንፈሴ ፡ እንጂ ፡ በኀይልና ፡
በብርታት ፡ አይደለም ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

7 ፤ ታላቅ ፡ ተራራ ፡ ሆይ ፥ አንተ ፡ ምንድር ፡ ነኽ ፡ በዘሩባቤል ፡ ፊት ፡ ደልዳላ ፡ ሜዳ ፡
ትኾናለኽ ፤ ሰዎችም ፦ ሞገስ ፥ ሞገስ ፡ ይኹንለት ፡ ብለው ፡ እየጮኹ ፡ ርሱ ፡ መደምደሚያውን ፡ ድንጋይ ፡ ያወጣል ፡
ብሎ ፡ ተናገረኝ ።

8 ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፦

9 ፤ የዘሩባቤል ፡ እጆች ፡ ይህን ፡ ቤት ፡ መሠረቱ ፥ የርሱም ፡ እጆች ፡ ይፈጽሙታል ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡
ወደ ፡ እናንተ ፡ እንደ ፡ ላከኝ ፡ ታውቃላችኹ ።

10 ፤ የጥቂቱን ፡ ነገር ፡ ቀን ፡ የናቀ ፡ ማን ፡ ነው ፡ እነዚህ ፡ ሰባቱ ፡ ደስ ፡ ብሏቸው ፡ በዘሩባቤል ፡ እጅ ፡ ቱንቢውን ፡
ያያሉ ፤ እነዚህም ፡ በምድር ፡ ኹሉ ፡ የሚዘዋወሩ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ዐይኖች ፡ ናቸው ።

11 ፤ እኔም ፡ መልሼ ፦ በመቅረዙ ፡ በስተቀኝና ፡ በስተግራ ፡ ያሉ ፡ እነዚህ ፡ ኹለት ፡ የወይራ ፡ ዛፎች ፡ ምንድር ፡

ናቸው ፦ አልኹት ።

12 ፤ ኹለተኛም ፡ መልሼ ፦ በኹለቱ ፡ የወርቅ ፡ ቧንቧዎች ፡ አጠገብ ፡ ኾነው ፡ የወርቁን ፡ ዘይት ፡ የሚያፈሱ ፡ እነዚህ ፡ ኹለት ፡ የወይራ ፡ ቅርንጫፎች ፡ ምንድር ፡ ናቸው ፦ አልኹት ።

13 ፤ ርሱም ፡ መልሶ ፦ እነዚህ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ኾኑ ፡ አታውቅምን ፦ አለኝ ። እኔም ፦ ጌታዬ ፡ ሆይ ፥ አላውቅም ፡ አልኹት ።

14 ፤ ርሱም ፦ በምድር ፡ ኹሉ ፡ ጌታ ፡ አጠገብ ፡ የቆሙት ፡ ኹለቱ ፡ የተቀቡት ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፡ አለኝ ።

ትንቢተ ፡ ዘካርያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 5 ።

ምዕራፍ ፡ 5 ።

1 ፤ ተመልሼም ፡ ዐይኖቼን ፡ አነሣኹ ፥ እንሆም ፥ አንድ ፡ በራሪ ፡ የመጽሐፍ ፡ ጥቅል ፡ አየኹ ።

2 ፤ ርሱም ፦ የምታየው ፡ ምንድር ፡ ነው ፦ አለኝ ። እኔም ፦ በራሪ ፡ የመጽሐፍ ፡ ጥቅል ፡ አያለኹ ፤ ርዝመቱ ፡ ኻያ ፡ ክንድ ፡ ወርዱም ፡ ዐሥር ፡ ክንድ ፡ ነው ፡ አልኹ ።

3 ፤ እንዲህም ፡ አለኝ ፦ ይህ ፡ በምድር ፡ ፊት ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፡ የሚወጣው ፡ ርግማን ፡ ነው ፤ የሚሰርቅ ፡ ኹሉ ፡ በርሱ ፡ ላይ ፡ በዚህ ፡ በኩል ፡ እንደተጻፈው ፡ ኹሉ ፡ ይጠፋል ፥ በሐሰት ፡ የሚምልም ፡ ኹሉ ፡ በርሱ ፡ ላይ ፡ በዚያ ፡ በኩል ፡ እንደተጻፈው ፡ ኹሉ ፡ ይጠፋል ።

4 ፤ እኔ ፡ አስወጣዋለኹ ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፥ ወደሚሰርቀውም ፡ ቤት ፥ በሐሰትም ፡ በስሜ ፡ ወደሚምለው ፡ ቤት ፡ ይገባል ፤ በቤቱም ፡ ውስጥ ፡ ይኖራል ፥ ርሱንም ፥ ዕንጨቱንና ፡ ድንጋዩን ፥ ይበላል ።

5 ፤ ከእኔም ፡ ጋራ ፡ ይነጋገር ፡ የነበረው ፡ መልአክ ፡ ወጥቶ ፦ ዐይኖችኽን ፡ አንሣ ፥ ይህችም ፡ የምትወጣው ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ኾነች ፡ እይ ፡ አለኝ ።

6 ፤ እኔም ፦ ምንድር ፡ ናት ፦ አልኹ ። ርሱም ፦ ይህች ፡ የምትወጣው ፡ የኢፍ ፡ መስፈሪያ ፡ ናት ፡ አለኝ ። ደግሞም ፦ በምድር ፡ ኹሉ ፡ ላይ ፡ ያለ ፡ በደላቸው ፡ ይህ ፡ ነው ፡ አለ ።

7 ፤ እንሆም ፥ የርሳሱን ፡ መክሊት ፡ አነሡት ፤ እንሆም ፥ በኢፍ ፡ መስፈሪያው ፡ ውስጥ ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ ተቀምጣ ፡ ነበር ።

8 ፤ ርሱም ፦ ይህች ፡ ክፋት ፡ ናት ፡ አለኝ ፤ በኢፍ ፡ መስፈሪያው ፡ ውስጥ ፡ ጣላት ፥ የርሳሱንም ፡ ጠገራ ፡ በመስፈሪያ ፡ አፍ ፡ ላይ ፡ ጣለ ።

9 ፤ ዐይኖቼንም ፡ አንሥቼ ፡ አየኹ ፥ እንሆም ፥ ኹለት ፡ ሴቶች ፡ ወጡ ፥ ነፋስም ፡ በክንፎቻቸው ፡ ነበረ ፤ ክንፎቻቸውም ፡ እንደ ፡ ሽመላ ፡ ክንፎች ፡ ነበሩ ፤ የኢፍ ፡ መስፈሪያውንም ፡ በምድርና ፡ በሰማይ ፡ መካከል ፡ አነሡት ።

10 ፤ ከእኔም ፡ ጋራ ፡ ይነጋገር ፡ የነበረውን ፡ መልአክ ፦ እነዚህ ፡ የኢፍ ፡ መስፈሪያውን ፡ ወዴት ፡ ይወስዱታል ፦ አልኹት ።

11 ፤ ርሱም ፦ በሰናዖር ፡ ምድር ፡ ቤት ፡ ይሠሩለት ፡ ዘንድ ፡ ይወስዱታል ፤ በተዘጋጀም ፡ ጊዜ ፡ በዚያ ፡ በስፍራው ፡ ይኖራል ፡ አለኝ ።

ትንቢተ ፡ ዘካርያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 6 ።

ምዕራፍ ፡ 6 ።

1 ፤ ተመልሼም ፡ ዐይኖቼን ፡ አነሣኹ ፥ እንሆም ፥ አራት ፡ ሠረገላዎች ፡ ከኹለት ፡ ተራራ ፡ መካከል ፡ ሲወጡ ፡ አየኹ ፤ ተራራዎቹም ፡ የናስ ፡ ተራራዎች ፡ ነበሩ ።

2 ፤ በፊተኛው ፡ ሠረገላ ፡ መጋላ ፡ ፈረሶች ፥ በኹለተኛውም ፡ ሠረገላ ፡ ዱሪ ፡ ፈረሶች ፡ ነበሩ ፥

3 ፤ በሦስተኛውም ፡ ሠረገላ ፡ ዐምባላይ ፡ ፈረሶች ፥ በአራተኛውም ፡ ሠረገላ ፡ ቅጥልጣል ፡ ፈረሶች ፡ ነበሩ ።

4 ፤ ከእኔ ፡ ጋራ ፡ ይነጋገር ፡ ለነበረውም ፡ መልአክ ፡ መልሼ ፦ ጌታዬ ፡ ሆይ ፥ እነዚህ ፡ ምንድር ፡ ናቸው ፦ አልኹት ።

5 ፤ መልአኩም ፡ መልሶ ፦ እነዚህ ፡ በምድር ፡ ኹሉ ፡ ጌታ ፡ ፊት ፡ ከቆሙበት ፡ ስፍራ ፡ የሚወጡ ፡ አራቱ ፡ የሰማይ ፡ ነፋሳት ፡ ናቸው ።

6 ፤ ዱሪ ፡ ፈረሶች ፡ ያሉበት ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ ይወጣል ፤ ዐምባላዮቹም ፡ ከነርሱ ፡ በኋላ ፡ ይወጣሉ ፥ ቅጥልጣሎችም ፡ ወደ ፡ ደቡብ ፡ ይወጣሉ ፡ አለኝ ።

7 ፤ መጋላዎቹም ፡ ደግሞ ፡ ወጡ ፡ በምድርም ፡ ይመላለሱ ፡ ዘንድ ፡ ለመኼድ ፡ ይፈልጉ ፡
ነበር ፤ ርሱም ፦ ኺዱ ፥ በምድር ፡ ላይ ፡ ተመላለሱ ፡ አለ ። እነርሱም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ተመላለሱ ።

8 ፤ ጮኾም ፦ እንሆ ፥ ወደሰሜን ፡ ምድር ፡ የሚወጡት ፡ እነርሱ ፡ መንፈሴን ፡ በሰሜን ፡ ምድር ፡ ላይ ፡ አሳርፈዋል ፡ ብሎ ፡ ተናገረኝ ።

9 ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፦

10 ፤ ከባቢሎን ፡ ከመጡት ፡ ምርኮኛዎች ፡ ከሔልዳይና ፡ ከጦብያ ፡ ከዮዳዔም ፡ ውሰድ ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ መጥተኽ ፡ ወደሰፎንያስ ፡ ልጅ ፡ ወደኢዮስያስ ፡ ቤት ፡ ግባ ።

11 ፤ ብርንና ፡ ወርቅን ፡ ከነርሱ ፡ ውሰድ ፥ አክሊሎችንም ፡ ሥራ ፤ በታላቁም ፡ ካህን ፡ በኢዮሴዴቅ ፡ ልጅ ፡ በኢያሱ ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ድፋቸው ፥

12 ፤ እንዲህም ፡ በለው ፦ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ እንሆ ፥ ስሙ ፡ ቍጥቋጥ ፡ የሚባል ፡ ሰው ፡ በስፍራው ፡ ይበቅላል ፥ የእግዚአብሔርንም ፡ መቅደስ ፡ ይሠራል ።

13 ፤ ርሱ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መቅደስ ፡ ይሠራል ፥ ክብርንም ፡ ይሸከማል ፥ በዙፋኑም ፡ ላይ ፡ ተቀምጦ ፡
ይነግሣል ፤ በዙፋኑም ፡ ላይ ፡ ካህን ፡ ይኾናል ፥ የሰላምም ፡ ምክር ፡ በኹለቱ ፡ መካከል ፡ ይኾናል ።

14 ፤ አክሊሎችም ፡ ለሔሌምና ፡ ለጦብያ ፡ ለዮዳዔም ፡ ለሶፎንያስም ፡ ልጅ ፡ ለሔን ፡ በእግዚአብሔር ፡ መቅደስ ፡ ውስጥ ፡ ለመታሰቢያ ፡ ይኾናሉ ።

15 ፤ በሩቅም ፡ ያሉት ፡ መጥተው ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መቅደስ ፡ ይሠራሉ ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ እንደ ፡ ላከኝ ፡ ታውቃላችኹ ። የአምላካችኹንም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ አጥብቃችኹ ፡ ብትሰሙ ፡ ይህ ፡ ይኾናል ።

## ትንቢተ ፡ ዘካርያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 7 ።

ምዕራፍ ፡ 7 ።

1 ፤ በንጉሡም ፡ በዳርዮስ ፡ በአራተኛው ፡ ዓመት ፡ ካሴሉ ፡ በሚባል ፡ በዘጠነኛው ፡ ወር ፡ በአራተኛው ፡ ቀን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ ዘካርያስ ፡ መጣ ።

2 ፤ የቤቴልም ፡ ሰዎች ፡ ሳራሳርንና ፡ ሬጌሜሌክን ፡ ሰዎቻቸውንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ይለምኑ ፡ ዘንድ ፥

3 ፤ ለሰራዊት ፡ ጌታ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ካህናት ፡ ለነቢያትም ፦ ባለፉት ፡ ዓመታት ፡ እንዳደረግኹት ፡
በዐምስተኛው ፡ ወር ፡ መለየትና ፡ ማልቀስ ፡ ይገባኛልን ፧ ብለው ፡ ይናገሩ ፡ ዘንድ ፡ ልኳቸው ፡ ነበር ።

4 ፤ የሰራዊትም ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፦

5 ፤ ለምድሩ ፡ ሕዝብ ፡ ኹሉ ፡ ለካህናትም ፡ እንዲህ ፡ ብለኽ ፡ ተናገራቸው ፦ በዚህ ፡ በሰባው ፡ ዓመት ፡ በዐምስተኛውና ፡ በሰባተኛው ፡ ወር ፡ በጾማችኹና ፡ ባለቀሳችኹ ፡ ጊዜ ፥ በእውኑ ፡ ለእኔ ፡ ጾም ፡ ጾማችኹልኝ ፧

6 ፤ በምትበሉበትና ፡ በምትጠጡበትስ ፡ ጊዜ ፥ ለራሳችኹ ፡ የምትበሉና ፡ የምትጠጡ ፡ አይደላችኹምን ፧

7 ፤ ኢየሩሳሌምና ፡ በዙሪያዋ ፡ ያሉ ፡ ከተማዎች ፡ ገና ፡ ሰዎች ፡ ባሉባቸው ፡ ጊዜ ፥ በምቾትም ፡ ተቀምጠው ፡
ሳሉ ፥ ደቡብና ፡ ቈላውም ፡ ሰዎች ፡ ባሉባቸው ፡ ጊዜ ፥ እግዚአብሔር ፡ በቀደሙት ፡ ነቢያት ፡ እጅ ፡ የተናገረውን ፡ ቃል ፡ መስማት ፡ አይገባችኹምን ፧

8 ፤ የእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ ዘካርያስ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፦

9 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናግሯል ፦ እውነተኛውን ፡ ፍርድ ፡ ፍረዱ ፤ ቸርነትንና ፡
ምሕረትን ፡ ሁላችኹ ፡ ለወንድሞቻችኹ ፡ አድርጉ ፤

10 ፤ መበለቲቱንና ፡ ድኻ ፡ አደጉን ፥ መጻተኛውንና ፡ ችግረኛውን ፡ አትበድሉ ፤ ከእናንተም ፡ ማንም ፡ በወንድሙ ፡
ላይ ፡ ክፉውን ፡ ነገር ፡ በልቡ ፡ አያስብ ።

11 ፤ እነርሱ ፡ ግን ፡ ደንደሳቸውን ፡ አዞሩ ፡ እንጂ ፡ መስማትን ፡ እምቢ ፡ አሉ ፤ እንዳይሰሙም ፡ ዦሯቸውን ፡ አደነቈሩ ።

12 ፤ የሰራዊትም ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ በቀደሙት ፡ ነቢያት ፡ እጅ ፡ በመንፈሱ ፡ የላከውን ፡ ሕጉንና ፡ ቃሉን ፡
እንዳይሰሙ ፡ ልባቸውን ፡ እንደ ፡ አልማዝ ፡ አጠነከሩ ፤ ስለዚህ ፥ ከሰራዊት ፡ ጌታ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ታላቅ ፡
ቍጣ ፡ መጣ ።

13 ፤ እኔ ፡ በጠራኹ ፡ ጊዜ ፡ እነርሱ ፡ እንዳልሰሙኝ ፥ እንዲሁ ፡ እነርሱ ፡ በሚጠሩበት ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ አልሰማም ፥ ይላል ፡
የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤

14 ፤ ወደማያውቋቸውም ፡ አሕዛብ ፡ ኹሉ ፡ በዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ በተንኳቸው ። እንዲሁ ፡ ከነርሱ ፡ በኋላ ፡ ምድሪቱ ፡
ባድማ ፡ ኾናለች ፥ የሚተላለፍባትና ፡ የሚመላለስባትም ፡ አልነበረም ፤ ያማረችውንም ፡ ምድር ፡ ባድማ ፡ አደረጓት ።

ትንቢተ ፡ ዘካርያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 8 ።

ምዕራፍ ፡ 8 ።

1 ፤ የሰራዊትም ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፦

2 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ስለ ፡ ጽዮን ፡ ታላቅ ፡ ቅንአት ፡ ቀንቻለኹ ፥ በታላቅም ፡ ቍጣ ፡
ስለ ፡ ርሷ ፡ ቀንቻለኹ ።

3 ፤ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ወደ ፡ ጽዮን ፡ ተመልሻለኹ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ መካከል ፡
እኖራለኹ ፤ ኢየሩሳሌምም ፡ የእውነት ፡ ከተማ ፡ ትባላለች ፤ የሰራዊትም ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ተራራ ፡ የተቀደሰ ፡
ተራራ ፡ ይባላል ።

4 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ ዳግመኛ ፡ ሽማግሌዎችና ፡ ባልቴቶች ፡ በኢየሩሳሌም ፡
አደባባይ ፡ ይቀመጣሉ ፤ ሰውም ፡ ኹሉ ፡ ከዕድሜው ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ ምርኵዝ ፡ በእጁ ፡ ይይዛል ።

5 ፤ የከተማዪቱም ፡ አደባባዮች ፡ በእነዚያ ፡ በሚጫወቱ ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ይሞላሉ ።

6 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ በዚህ ፡ ወራት ፡ በዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ቅሬታ ፡ ዐይን ፡ ዘንድ ፡ ድንቅ ፡
ቢኾን ፥ በእውኑ ፡ በእኔ ፡ ዐይን ፡ ዘንድ ፡ ደግሞ ፡ ድንቅ ፡ ይኾናልን ፧ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

7 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ እንሆ ፥ ሕዝቤን ፡ ከምሥራቅ ፡ ምድርና ፡ ከምዕራብ ፡ ምድር ፡
አድንነዋለኹ ፤

8 ፤ አመጣቸዋለኹም ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ ውስጥ ፡ ይኖራሉ ፤ እነርሱም ፡ ሕዝብ ፡ ይኾኑኛል ፥ እኔም ፡ በእውነትና ፡
በጽድቅ ፡ አምላክ ፡ እኾናቸዋለኹ ።

9 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ መቅደሱ ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔር ፡
ቤት ፡ ከተመሠረተበት ፡ ቀን ፡ ዠምሮ ፡ ከነቢያት ፡ አፍ ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ በዚህ ፡ ዘመን ፡ የሰማችኹ ፡ እናንተ ፡
ሆይ ፥ እጃችኹን ፡ አበርቱ ።

10 ፤ ከዚያ ፡ ወራት ፡ አስቀድሞ ፡ ለሰውና ፡ ለእንስሳ ፡ ዋጋ ፡ አልነበረምና ፤ እኔም ፡ ሰውን ፡ ኹሉ ፡ በወንድሙ ፡ ላይ ፡
አስነሥቼ ፡ ነበርና ፥ ካስጨናቂው ፡ የተነሣ ፡ ለሚገባውና ፡ ለሚወጣው ፡ ሰላም ፡ አልነበረም ።

11 ፤ አኹን ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ቀደመው ፡ ዘመን ፡ በዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ቅሬታ ፡ ላይ ፡ አልኾንም ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔር ።

12 ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ሰላምን ፡ እዘራለኹ ፤ ወይኑ ፡ ፍሬውን ፡ ይሰጣል ፥ ምድርም ፡ አዝመራዋን ፡ ታወጣለች ፥ ሰማያትም ፡
ጠላቸውን ፡ ይሰጣሉ ፤ ለዚህም ፡ ሕዝብ ፡ ቅሬታ ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ኹሉ ፡ አወርሳለኹ ።

13 ፤ የይሁዳ ፡ ቤትና ፡ የእስራኤል ፡ ቤት ፡ ሆይ ፥ በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ ርግማን ፡ እንደ ፡ ነበራችኹ ፥ እንዲሁ ፡
አድናችኋለኹ ፥ በረከትም ፡ ትኾናላችኹ ፤ አትፍሩ ፥ እጃችኹንም ፡ አበርቱ ።

14 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላልና ፦ አባቶቻችኹ ፡ እጅግ ፡ ባስቈጡኝ ፡ ጊዜ ፡ ክፉ ፡ ለማድረግ ፡
እንዳሰብኹ ፥ እንዳልተጸጸትኹም ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፥

15 ፤ እንዲሁ ፡ ዳግመኛ ፡ ለኢየሩሳሌምና ፡ ለይሁዳ ፡ ቤት ፡ በዚህ ፡ ወራት ፡ በጎነትን ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡
ዐስቤያለኹ ፤ አትፍሩ ።

16 ፤ የምትሠሩት ፡ ነገር ፡ ይህ ፡ ነው ፤ እያንዳንዳችኹ ፡ ከባልንጀራችኹ ፡ ጋራ ፡ እውነትን ፡ ተነጋገሩ ፤ በበር ፡
አደባባያችኹም ፡ የእውነትንና ፡ የሰላምን ፡ ፍርድ ፡ ፍረዱ ፤

17 ፤ ኹላችኹም ፡ በባልንጀራችኹ ፡ ላይ ፡ ክፉን ፡ ነገር ፡ በልባችኹ ፡ አታስቡ ፤ የሐሰትንም ፡ መሐላ ፡
አትውደዱ ፤ ይህን ፡ ነገር ፡ ኹሉ ፡ እጠላለኹና ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

18 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ሲል ፡ መጣ ፦

19 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ የአራተኛው ፡ ወር ፡ ጾም ፡ የዐምስተኛውም ፡ የሰባተኛውም ፡
የዐሥረኛውም ፡ ወር ፡ ጾም ፡ ለይሁዳ ፡ ቤት ፡ ደስታና ፡ ተድላ ፡ የሐሤትም ፡ በዓላት ፡ ይኾናል ፤ ስለዚህም ፡ እውነትንና ፡
ሰላምን ፡ ውደዱ ።

20 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ በብዙ ፡ ከተማዎች ፡ የሚቀመጡ ፡ አሕዛብ ፡ ገና ፡ ይመጣሉ ፤

21 ፤ በአንዲትም ፡ ከተማ ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፦ እግዚአብሔርን ፡ እንለምን ፡ ዘንድ ፥ የሰራዊትንም ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔርን ፡ እንፈልግ ፡ ዘንድ ፡ ኑ ፡ እንኺድ ፤ እኔም ፡ እኼዳለኹ ፡ እያሉ ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ከተማ ፡ ይኼዳሉ ።

22 ፤ ብዙ ፡ ወገኖችና ፡ ኀይለኛዎች ፡ አሕዛብ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የሰራዊትን ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ይፈልጉ ፡
ዘንድ ፥ እግዚአብሔርንም ፡ ይለምኑ ፡ ዘንድ ፡ ይመጣሉ ።

23 ፤ የሰራዊትም ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ በዚያ ፡ ዘመን ፡ ከአሕዛብ ፡ ቋንቋ ፡ ኹሉ ፡ ዐሥር ፡ ሰዎች ፡
የአንዱን ፡ አይሁዳዊ ፡ ሰው ፡ ልብስ ፡ ዘርፍ ፡ ይዘው ፦ እግዚአብሔር ፡ ከእናንተ ፡ ጋራ ፡ እንዳለ ፡ ሰምተናልና ፥ ከእናንተ ፡
ጋራ ፡ እንኺድ ፡ ይላሉ ።

## ትንቢተ ፡ ዘካርያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 9 ።

ምዕራፍ ፡ 9 ።

1 ፤ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ሸክም ፡ በሴድራክ ፡ ምድር ፡ ላይ ፡ ነው ፥ በደማስቆም ፡ ላይ ፡ ያርፋል ፤ የእግዚአብሔር ፡
ዐይን ፡ ወደ ፡ ሰውና ፡ ወደእስራኤል ፡ ነገድ ፡ ኹሉ ፡ ዘንድ ፡ ነው ፤

2 ፤ ደግሞም ፡ በዳርቻዋ ፡ ባለችው ፡ በሐማት ፡ ላይ ፥ እጅግ ፡ ጠቢበኛዎች ፡ በኾኑ ፡ በጢሮስና ፡ በሲዶና ፡ ላይ ፡ ነው ።

3 ፤ ጢሮስም ፡ ምሽግን ፡ ለራሷ ፡ ሠርታለች ፥ ብሩንም ፡ እንደ ፡ ዐፈር ፥ ጥሩውንም ፡ ወርቅ ፡ እንደ ፡ መንገድ ፡ ጭቃ ፡
አከማችታለች ።

4 ፤ እነሆ ፥ ጌታ ፡ ይገፋታል ፥ በባሕርም ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ ብርታቷን ፡ ይመታል ፤ ርሷም ፡ በእሳት ፡ ትበላለች ።

5 ፤ አስቀሎና ፡ አይታ ፡ ትፈራለች ፤ ጋዛ ፡ ደግሞ ፡ አይታ ፡ እጅግ ፡ ትታመማለች ፤ ዐቃሮንም ፡ እንዲሁ ፥ ተስፋዋ ፡
ይቈረጣልና ፤ ንጉሡም ፡ ከጋዛ ፡ ይጠፋል ፥ በአስቀሎናም ፡ የሚቀመጥ ፡ አይገኝም ።

6 ፤ የተደባለቀ ፡ ወገን ፡ በአዛጦን ፡ ይቀመጣል ፥ የፍልስጥኤማውያንንም ፡ ትዕቢት ፡ አጠፋለኹ ።

7 ፤ ደሙንም ፡ ከአፉ ፡ ውስጥ ፡ ርኩሱንም ፡ ነገር ፡ ከጥርሱ ፡ መካከል ፡ አስወግዳለኹ ፤ ርሱም ፡ ደግሞ ፡ ለአምላካችን ፡
ቅሬታ ፡ ይኾናል ፤ በይሁዳም ፡ እንደ ፡ አለቃ ፡ ይኾናል ፥ ዐቃሮንም ፡ እንደ ፡ ኢያቡሳዊ ፡ ይኾናል ።

8 ፤ እኔም ፡ ማንም ፡ እንዳይኼድና ፡ እንዳይመለስ ፡ እንደ ፡ ጠባቂ ፡ ጦር ፡ ኾኜ ፡ በቤቴ ፡ ዙሪያ ፡ ሰፈር ፡
አደርጋለኹ ፤ አኹንም ፡ በዐይኔ ፡ አይቻለኹና ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አስጨናቂ ፡ አያልፍባቸውም ።

9 ፤ አንቺ ፡ የጽዮን ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ እጅግ ፡ ደስ ፡ ይበልሽ ፤ አንቺ ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፥ እልል ፡
በዪ ፤ እንሆ ፥ ንጉሥሽ ፡ ጻድቅና ፡ አዳኝ ፡ ነው ፤ ትሑትም ፡ ኾኖ ፡ በአህያም ፥ በአህያዪቱ ፡ ግልገል ፡ በውርንጫዪቱ ፡
ላይ ፡ ተቀምጦ ፡ ወደ ፡ አንቺ ፡ ይመጣል ።

10 ፤ ሠረገላውንም ፡ ከኤፍሬም ፡ ፈረሱንም ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ አጠፋለኹ ፤ የሰልፉም ፡ ቀስት ፡ ይሰበራል ፥ ለአሕዛብም ፡
ሰላምን ፡ ይናገራል ፤ ግዛቱም ፡ ከባሕር ፡ እስከ ፡ ባሕር ፥ ከወንዙም ፡ እስከምድር ፡ ዳርቻ ፡ ድርስ ፡ ይኾናል ።

11 ፤ ላንቺም ፡ ደግሞ ፡ ስለ ፡ ቃል ፡ ኪዳንሽ ፡ ደም ፥ እስሮችሽን ፡ ውሃ ፡ ከሌለበት ፡ጕድጓድ ፡ አውጥቻለኹ ።

12 ፤ እናንተ ፡ በተስፋ ፡ የምትኖሩ ፡ እስሮች ፡ ሆይ ፥ ወደ ፡ ጽኑ ፡ ዐምባ ፡ ተመለሱ ፤ ኹለት ፡ ዕጥፍ ፡ አድርጌ ፡
እንድመልስልሽ ፡ ዛሬ ፡ እነግርሻለኹ ።

13 ፤ ይሁዳን ፡ ለእኔ ፡ ገትሬያለኹ ፤ ቀስቱን ፡ በኤፍሬም ፡ ሞልቻለኹ ፤ ጽዮን ፡ ሆይ ፥ ልጆችሽን ፡ በግሪክ ፡ ልጆች ፡
ላይ ፡ አስነሣለኹ ፥ አንቺንም ፡ እንደ ፡ ኀያል ፡ ሰው ፡ ሰይፍ ፡ አደርግሻለኹ ።

14 ፤ እግዚአብሔርም ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ይገለጣል ፥ ፍላጻውም ፡ እንደ ፡ መብረቅ ፡ ይወጣል ፤ ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡
መለከትን ፡ ይነፋል ፥ በደቡብም ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ ይኼዳል ።

15 ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይጠብቃቸዋል ፤ እነርሱም ፡ ይበሏቸዋል ፥ የወንጭፉንም ፡ድንጋዮች ፡
ይረግጣሉ ፤ እንደ ፡ ወይን ፡ ጠጅም ፡ ይጠጧቸዋል ፥ እንደ ፡ ጥዋዎችም ፡ እንደ ፡ መሠዊያም ፡ ማእዘኖች ፡ የተሞሉ ፡
ይኾናሉ ።

16 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ አምላካቸው ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሕዝቡ ፡ መንጋ ፡ ያድናቸዋል ፤ እነርሱም ፡ ለአክሊል ፡
እንደሚኾኑ ፡ እንደ ፡ ከበሩ ፡ ድንጋዮች ፡ ይኾናሉ ፥ በምድሩም ፡ ላይ ፡ ይብለጨለጫሉ ።

17 ፤ በጎነቱ ፡ እንዴት ፡ ታላቅ ፡ ነው! ውበቱስ ፡ እንዴት ፡ ታላቅ ፡ ነው! እኽል ፡ጕበዛዝቱን ፥ ጕሽ ፡ ጠጅም ፡
ቈነጃጅቱን ፡ ያለመልማል ።

ትንቢተ ፡ ዘካርያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 10 ።

ምዕራፍ ፡ 10 ።

1 ፤ በኋለኛው ፡ ዝናብ ፡ ጊዜ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ዝናቡን ፡ ለምኑ ፤ እግዚአብሔር ፡ መብረቅ ፡
ያደርጋል ፤ ርሱም ፡ የበልግ ፡ ዝናብን ፡ ለያንዳንዱም ፡ በሜዳ ፡ ውስጥ ፡ ሣርን ፡ ይሰጣል ።

2 ፤ ተራፊም ፡ ከንቱነትን ፡ ተናግረዋልና ፥ ሟርተኛዎችም ፡ ውሸትን ፡ አይተዋልና ፤ ሕልምንም ፡ የሚያዩ ፡ በሐሰት ፡
ተናግረዋል ፥ በከንቱም ፡ ያጽናናሉ ፤ እረኛም ፡ የላቸውምና ፡ እንደ ፡ በጎች ፡ ተቅበዝብዘዋል ፡ ተጨንቀውማል ።

3 ፤ ቍጣዬ ፡ በእረኛዎች ፡ ላይ ፡ ነዷል ፥ አውራ ፡ ፍየሎችንም ፡ እቀጣለኹ ፤ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡
የይሁዳን ፡ ቤት ፡ መንጋውን ፡ ጐብኝቷል ፥ በሰልፍም ፡ ውስጥ ፡ እንዳለ ፡ እንደ ፡ ክብሩ ፡ ፈረስ ፡ ያደርጋቸዋል ።

4 ፤ ከርሱ ፡ ዘንድ ፡ የማእዘኑ ፡ ድንጋይ ፥ ከርሱም ፡ ዘንድ ፡ ችንካሩ ፥ ከርሱም ፡ ዘንድ ፡ የሰልፉ ፡ ቀስት ፥ ከርሱም ፡
ዘንድ ፡ አስገባሪው ፡ ኹሉ ፡ ባንድ ፡ ላይ ፡ ይመጣሉ ።

5 ፤ በሰልፍም ፡ ጊዜ ፡ ጠላቶቻቸውን ፡ በመንገድ ፡ ጭቃ ፡ ውስጥ ፡ እንደሚረግጡ ፡ ኀያላን ፡ ይኾናሉ ፤ እግዚአብሔርም ፡
ከነርሱ ፡ ጋራ ፡ ነውና ፥ ይዋጋሉ ፥ ፈረሰኛዎችም ፡ ያፍራሉ ።

6 ፤ ወድጃቸዋለኹና ፡ የይሁዳን ፡ ቤት ፡ አበረታለኹ ፥ የዮሴፍንም ፡ ቤት ፡
አድናለኹ ፤ አደላድላቸዋለኹም ፤ እመልሳቸዋለኹ ፤ እኔም ፡ አምላካቸው ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝና ፥ እኔም ፡
እሰማቸዋለኹና ፡ እንዳልጣልኋቸው ፡ ይኾናሉ ።

7 ፤ የኤፍሬምም ፡ ሰዎች ፡ እንደ ፡ ኀያላን ፡ ይኾናሉ ፥ ልባቸውም ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ እንደ ፡ ጠጣ ፡ ሰው ፡ ደስ ፡
ይለዋል ፤ ልጆቻቸውም ፡ አይተው ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፥ ልባቸውም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ሐሤት ፡ ያደርጋል ።

8 ፤ ተቤዥቻቸዋለኹና ፡ በፉጨት ፡ ጠርቼ ፡ እሰበስባቸዋለኹ ፤ ቀድሞም ፡ በዝተው ፡ እንደ ፡ ነበሩ ፡ ይበዛሉ ።

9 ፤ በአሕዛብም ፡ መካከል ፡ብዘራቸው ፡ እንኳ ፡ በሩቅ ፡ አገር ፡ ሳሉ ፡ ያስቡኛል ፥ ከልጆቻቸውም ፡ ጋራ ፡ በሕይወት ፡

ይኖራሉ ፥ ይመለሱማል ።

10 ፤ ከግብጽም ፡ ምድር ፡ እመልሳቸዋለኹ ፥ ከአሶርም ፡ እሰበስባቸዋለኹ ፤ ወደ ፡ ገለዓድና ፡ ወደሊባኖስ ፡ ምድር ፡ አመጣቸዋለኹ ፥ የሚበቃም ፡ ቦታ ፡ አይገኝላቸውም ።

11 ፤ ርሱም ፡ በጭንቅ ፡ ባሕር ፡ ያልፋል ፥ የባሕርንም ፡ ሞገድ ፡ ይመታል ፥ የወንዙም ፡ ጥልቅ ፡ ዅሉ ፡ ይደርቃል ፤ የአሶርም ፡ ትዕቢት ፡ ይዋረዳል ፥ የግብጽም ፡ በትረ ፡ መንግሥት ፡ ይርቃል ።

12 ፤ በአምላካቸው ፡ በእግዚአብሔር ፡ አበረታቸዋለኹ ፥ በስሙም ፡ ይመካሉ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

## ትንቢተ ፡ ዘካርያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 11 ።

ምዕራፍ ፡ 11 ።

1 ፤ ሊባኖስ ፡ ሆይ ፥ ደጆችኽን ፡ ክፈት ፥ እሳትም ፡ ዝግባዎችኽን ፡ ትብላ ።

2 ፤ የጥድ ፡ ዛፍ ፡ ሆይ ፥ ዝግባ ፡ ወድቋልና ፥ ከበርቴዎችም ፡ ጠፍተዋልና ፥ ዋይ ፡ በል ፤ እናንተም ፡ የባሳን ፡ ዛፎች ፡ ሆይ ፥ ጽኑው ፡ ጫካ ፡ ተቈርጧልና ፥ ዋይ ፡ በሉ ።

3 ፤ የእረኛዎች ፡ ክብር ፡ ተዋርዷልና ፥ የዋይታቸው ፡ ድምፅ ፡ ተሰምቷል ፤ የዮርዳኖስ ፡ ትዕቢት ፡ ተዋርዷልና ፥ የአንበሳዎች ፡ ግሣት ፡ ድምፅ ፡ ተሰምቷል ።

4 ፤ አምላኬ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ብሏል ፦ ለዕርድ ፡ የሚኾኑትን ፡ በጎች ፡ ጠብቅ ።

5 ፤ የገዟቸው ፡ ያርዷቸዋል ፥ ራሳቸውንም ፡ እንደ ፡ በደለኛዎች ፡ አድርገው ፡ አይቈጥሩም ፤ የሸጧቸውም ፦ ባለጠጋ ፡ ኾነናልና ፥ እግዚአብሔር ፡ ይመስገን ፡ ይላሉ ፤ እረኛዎቻቸውም ፡ አይራሩላቸውም ።

6 ፤ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ለሚኖሩ ፡ አልራራም ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ እንሆም ፥ ሰውን ፡ ዅሉ ፡ በባልንጀራውና ፡ በንጉሡ ፡ እጅ ፡ አሳልፌ ፡ እሰጣለኹ ፤ ምድሪቱንም ፡ ይመታሉ ፥ ከእጃቸውም ፡ አላድናቸውም ።

7 ፤ እኔም ፡ ለዕርድ ፡ የሚኾኑትን ፡ በጎች ፥ የመንጋውን ፡ ችግረኛዎች ፡ ጠበቅኹ ። ኹለት ፡ በትሮችንም ፡ ወሰድኹ ፤ የአንዷቱን ፡ ስም ፡ ውበት ፡ የኹለተኛዪቱንም ፡ ስም ፡ ማሰሪያ ፡ ብዬ ፡ ጠራኹ ፤ መንጋውንም ፡ ጠበቅኹ ።

8 ፤ ባንድ ፡ ወርም ፡ ሦስቱን ፡ እረኛዎች ፡ አጠፋኹ ፤ ነፍሴም ፡ ተሰቀቀቻቸው ፥ ነፍሳቸውም ፡ ደግሞ ፡ እኔን ፡ ጠላች ።

9 ፤ እኔም ፦ እናንተን ፡ አልጠብቅም ፤ የሚሞተው ፡ ይሙት ፥ የሚጠፋውም ፡ ይጥፋ ፤ የቀረውም ፡ እያንዳንዱ ፡ የባልንጀራውን ፡ ሥጋ ፡ ይብላ ፡ አልኹ ።

10 ፤ እኔም ፡ ከሕዝቦች ፡ ዅሉ ፡ ጋራ ፡ የገባኹትን ፡ ቃል ፡ኪዳኔን ፡ አፈርስ ፡ ዘንድ ፡ ውበት ፡ የተባለችውን ፡ በትሬን ፡ ወስጄ ፡ ቈረጥኹ ።

11 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ ተሰበረች ፤ እንዲሁም ፡ እኔን ፡ የተመለከቱ ፡ የመንጋው ፡ ችግረኛዎች ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ ዐወቁ ።

12 ፤ እኔም ፦ ደስ ፡ ብሏችኹ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ ዋጋዬን ፡ስጡኝ ፤ ያለዚያ ፡ ግን ፡ ተዉት ፡ አልኹ ። እነርሱም ፡ ለዋጋዬ ፡ ሠላሳ ፡ ብር ፡ መዘኑ ።

13 ፤ እግዚአብሔርም ፦ የተስማሙበትን ፡ የከበረውን ፡ ዋጋዬን ፡ በግምጃ ፡ ቤቱ ፡ ውስጥ ፡ አኑረው ፡ አለኝ ። እኔም ፡ ሠላሳውን ፡ ብር ፡ ወስጄ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ባለው ፡ በግምጃ ፡ ቤቱ ፡ ውስጥ ፡ አኖርኹት ።

14 ፤ በይሁዳና ፡ በእስራኤል ፡ መካከል ፡ ያለውንም ፡ ወንድማማችነት ፡ እሰብር ፡ ዘንድ ፡ ማሰሪያ ፡ የተባለችውን ፡ ኹለተኛዪቱን ፡ በትሬን ፡ ቈረጥኹ ።

15 ፤ እግዚአብሔርም ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፦ ዳግመኛም ፡ የሰነፍን ፡ እረኛ ፡ ዕቃ ፡ ውሰድ ።

16 ፤ እንሆ ፥ በአገሩ ፡ ውስጥ ፡ እረኛ ፡ አስነሣለኹ ፤ ርሱም ፡ የጠፋውን ፡ አያስብም ፥ የባዘነውን ፡ አይፈልግም ፥ የተሰበረውን ፡ አይጠግንም ፤ የዳነውንም ፡ አይቀልብም ፥ ነገር ፡ ግን ፥ የሰባውን ፡ ሥጋ ፡ ይበላል ፥ ሰኰናውንም ፡ ይቀለጣጥማል ።

17 ፤ መንጋውን ፡ ለሚተው ፡ ለምናምንቴ ፡ እረኛ ፡ ወዮለት! ሰይፍ ፡ በክንዱና ፡ በቀኝ ፡ ዐይኑ ፡ ላይ ፡ ይኾናል ፤ ክንዱም ፡
አጥብቃ ፡ ትደርቃለች ፥ ቀኝ ፡ ዐይኑም ፡ ፈጽሞ ፡ ትጨልማለች ።

ትንቢ.ተ ፡ ዘካርያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 12 ።

ምዕራፍ ፡ 12 ።

1 ፤ ስለ ፡ እስራኤል ፡ የተነገረ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ሸክም ፡ ይህ ፡ ነው ፦ ሰማያትን ፡ የዘረጋ ፥ ምድርንም ፡
የመሠረተ ፥ የሰውንም ፡ መንፈስ ፡ በውስጡ ፡ የሠራ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦

2 ፤ እንሆ ፥ ኢየሩሳሌምን ፡ በዙሪያዋ ፡ ላሉት ፡ ለአሕዛብ ፡ ኹሉ ፡ የመንገድገድ ፡ ዋንጫ ፡ አደርጋታለኹ ፤ ደግሞም ፡
ኢየሩሳሌም ፡ ስትከበብ ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ እንዲሁ ፡ ይኾናል ።

3 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ ለአሕዛብ ፡ ኹሉ ፡ ከባድ ፡ ድንጋይ ፡ አደርጋታለኹ ፤ የሚሸከሟት ፡ ኹሉ ፡ እጅግ ፡
ይቈስላሉ ፤ የምድርም ፡ አሕዛብ ፡ ኹሉ ፡ በላይዋ ፡ ላይ ፡ ይከማቻሉ ።

4 ፤ በዚያ ፡ ቀን ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፥ ፈረስን ፡ ኹሉ ፡ በድንጋጤ ፥ ተቀማጭንም ፡ በእብድነት ፡
እመታለኹ ፤ ዐይኖቼንም ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ እከፍታለኹ ፥ የአሕዛብንም ፡ ፈረሶች ፡ ኹሉ ፡ በዕውርነት ፡ እመታለኹ ።

5 ፤ የይሁዳም ፡ አለቃዎች ፡ በልባቸው ፦ በኢየሩሳሌም ፡ ለሚኖሩ ፡ በአምላካቸው ፡ በሰራዊት ፡ ጌታ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ብርታት ፡ አለ ፡ ይላሉ ።

6 ፤ በዚያ ፡ ቀን ፡ የይሁዳን ፡ አለቃዎች ፡ በዕንጨት ፡ መካከል ፡ እንዳለ ፡ ትንታግ ፥ በነዶዎችም ፡ መካከል ፡ እንዳለ ፡
እንደ ፡ ፋና ፡ ነበልባል ፡ አደርጋቸዋለኹ ፤ በቀኝና ፡ በግራ ፡ በዙሪያ ፡ ያሉትን ፡ አሕዛብ ፡ ኹሉ ፡ ይበላሉ ፤ ከዚያም ፡
ወዲያ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ በስፍራዋ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ትኖራለች ።

7 ፤ እግዚአብሔርም ፡ የዳዊት ፡ ቤት ፡ ክብርና ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ሰዎች ፡ ክብር ፡ በይሁዳ ፡ ክብር ፡ ላይ ፡ እንዳይታበይ ፡
የይሁዳን ፡ ድንኳኖች ፡ አስቀድሞ ፡ ያድናል ።

8 ፤ በዚያ ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ለሚኖሩት ፡ ይመክትላቸዋል ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ ከነርሱ ፡ መካከል ፡
ደካማው ፡ እንደ ፡ ዳዊት ፡ ይኾናል ፤ የዳዊትም ፡ ቤት ፡ በፊታቸው ፡ እንደእግዚአብሔር ፡ መልአክ ፡ እንደ ፡ አምላክ ፡
ይኾናል ።

9 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ላይ ፡ የሚመጡትን ፡ አሕዛብ ፡ ኹሉ ፡ ለማጥፋት ፡ እጋደላለኹ ።

10 ፤ በዳዊትም ፡ ቤት ፡ ላይ ፥ በኢየሩሳሌምም ፡ በሚኖሩት ፡ ላይ ፥ የሞገስንና ፡ የልመናን ፡ መንፈስ ፡ አፈሳለኹ ፤ ወደ ፡
ርሱም ፡ ወደወጉት ፡ ይመለከታሉ ፤ ሰውም ፡ ለአንድያ ፡ ልጁ ፡ እንደሚያለቅስ ፡ ያለቅሱለታል ፥ ሰውም ፡ ለበኵር ፡ ልጁ ፡
እንደሚያዝን ፡ በመራራ ፡ ሐዘን ፡ ያዝኑለታል ።

11 ፤ በዚያ ፡ ቀን ፡ በመጊዶን ፡ ሜዳ ፡ እንደ ፡ ነበረው ፡ እንደ ፡ ሐዳድሪሞን ፡ ልቅሶ ፡ ታላቅ ፡ ልቅሶ ፡ በኢየሩሳሌም ፡
ይኾናል ።

12 ፤ ምድሪቱም ፡ ታለቅሳለች ፤ እያንዳንዱ ፡ ወገን ፡ ለብቻው ፥ የዳዊት ፡ ቤት ፡ ወገን ፡ ለብቻው ፥ ሴቶቻቸውም ፡
ለብቻቸው ፤ የናታን ፡ ቤት ፡ ወገን ፡ ለብቻው ፥ ሴቶቻቸውም ፡ ለብቻቸው ፤

13 ፤ የሌዊ ፡ ቤት ፡ ወገን ፡ ለብቻው ፥ ሴቶቻቸውም ፡ ለብቻቸው ፤ የሰሜኢ ፡ ወገን ፡ ለብቻው ፥ ሴቶቻቸውም ፡
ለብቻቸው ፤

14 ፤ የቀሩት ፡ ወገኖች ፡ ኹሉ ፡ እያንዳንዱ ፡ ወገን ፡ ለብቻው ፥ ሴቶቻቸውም ፡ ለብቻቸው ፡ ያለቅሳሉ ።

ትንቢ.ተ ፡ ዘካርያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 13 ።

ምዕራፍ ፡ 13 ።

1 ፤ በዚያ ፡ ቀን ፡ ለዳዊት ፡ ቤትና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ለሚኖሩ ፡ ከኀጢአትና ፡ ከርኵሰት ፡ የሚያነጻ ፡ ምንጭ ፡ ይከፈታል ።

2 ፤ በዚያ ፡ ቀን ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፥ የጣዖታትን ፡ ስም ፡ ከምድር ፡ አጠፋለኹ ፥ ከዚያም ፡ በኋላ ፡
አይታሰቡም ፤ ደግሞም ፡ ሐሰተኛዎችን ፡ ነቢያትና ፡ ርኩስ ፡ መንፈስን ፡ ከምድር ፡ ላይ ፡ አስወግዳለኹ ።

3 ፤ ማንም ፡ ደግሞ ፡ ትንቢት ፡ ቢናገር ፡ የወለዱት ፡ አባቱና ፡ እናቱ ፦ አንተ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ሐሰትን ፡
ተናግረኻልና ፥ በሕይወት ፡ አትኖርም ፡ ይሉታል ፤ ትንቢትንም ፡ ሲናገር ፡ የወለዱት ፡ አባቱና ፡ እናቱ ፡ ይወጉታል ።

4 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ ነቢያቱ ፡ ዅሉ ፡ ትንቢትን ፡ ሲናገሩ ፡ እያንዳንዱ ፡ ስለ ፡ ራእዩ ፡ ያፍራል ፤ ያታልሉም ፡ ዘንድ ፡
የማቅ ፡ ልብስ ፡ አይለብሱም ።

5 ፤ ርሱ ፡ ግን ፦ ከታናሽነቴ ፡ ዠምሮ ፡ ባሪያ ፡ ኾኜ ፡ ነበርኹና ፡ ገበሬ ፡ ሰው ፡ ነኝ ፡ እንጂ ፡ ነቢይ ፡ አይደለኹም ፡
ይላል ።

6 ፤ ሰውም ፦ ይህ ፡ በእጅኽ ፡ መካከል ፡ ያለ ፡ ቍስል ፡ ምንድር ፡ ነው ፡ ይለዋል ። ርሱም ፦ በወዳጆቼ ፡ ቤት ፡
የቈሰልኹት ፡ ቍስል ፡ ነው ፡ ይላል ።

7 ፤ ሰይፍ ፡ ሆይ ፥ ባልንጀራዬ ፡ በኾነው ፡ ሰው ፡ በእረኛዬ ፡ ላይ ፡ ንቃ ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔር ፤ እረኛውን ፡ ምታ ፥ በጎቹም ፡ ይበተናሉ ፤ እጄንም ፡ በታናናሾች ፡ ላይ ፡ እመልሳለኹ ።

8 ፤ በምድርም ፡ ዅሉ ፡ ላይ ፡ ኹለት ፡ ክፍል ፡ ተቈርጠው ፡ ይሞታሉ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ ሦስተኛውም ፡ ክፍል ፡
በርሷ ፡ ውስጥ ፡ ይቀራል ።

9 ፤ ሦስተኛውንም ፡ ክፍል ፡ ወደ ፡ እሳት ፡ አገባለኹ ፥ ብርም ፡ እንደሚነጥር ፡ አነጥራቸዋለኹ ፥ ወርቅም ፡ እንደሚፈተን ፡
እፈትናቸዋለኹ ፤ እነርሱም ፡ ስሜን ፡ ይጠራሉ ፥ እኔም ፡ እሰማቸዋለኹ ፤ እኔም ፦ ይህ ፡ ሕዝቤ ፡ ነው ፡
እላለኹ ፤ ርሱም ፦ እግዚአብሔር ፡ አምላኬ ፡ ነው ፡ ይላል ።

ትንቢተ ፡ ዘካርያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 14 ።

ምዕራፍ ፡ 14 ።

1 ፤ እነሆ ፥ የእግዚአብሔር ፡ ቀን ፡ ይመጣል ፥ ብዝበዛሽንም ፡ በውስጥሽ ፡ ይካፈላሉ ።

2 ፤ አሕዛብንም ፡ ዅሉ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ላይ ፡ ለሰልፍ ፡ እሰበስባለኹ ፤ ከተማዪቱም ፡ ትያዛለች ፥ ቤቶችም ፡
ይበዘበዛሉ ፥ ሴቶችም ፡ ይነወራሉ ፤ የከተማዪቱም ፡ እኩሌታ ፡ ለምርኮ ፡ ይወጣል ፥ የቀረው ፡ ሕዝብ ፡ ግን ፡ ከከተማ ፡
አይጠፋም ።

3 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ይወጣል ፥ በሰልፍም ፡ ቀን ፡ እንደ ፡ ተዋጋ ፡ ከነዚያ ፡ አሕዛብ ፡ ጋራ ፡ ይዋጋል ።

4 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ እግሮቹ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ትይዩ ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ባለው ፡ በደብረ ፡ ዘይት ፡ ላይ ፡
ይቆማሉ ፤ ደብረ ፡ ዘይትም ፡ በመካከል ፡ ወደ ፡ ምሥራቅና ፡ ወደ ፡ ምዕራብ ፡ ይሰነጠቃል ፥ እጅግም ፡ ታላቅ ፡ ሸለቆ ፡
ይኾናል ፤ የተራራውም ፡ እኩሌታ ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፥ እኩሌታውም ፡ ወደ ፡ ደቡብ ፡ ይርቃል ።

5 ፤ የተራራዎችም ፡ ሸለቆ ፡ እስከ ፡ አጸል ፡ ይደርሳልና ፥ በተራራዎች ፡ ሸለቆ ፡ ትሸሻላችኹ ፤ በይሁዳም ፡ ንጉሥ ፡
በዖዝያን ፡ ዘመን ፡ ከኾነው ፡ ከምድር ፡ መናወጥ ፡ ፊት ፡ እንደ ፡ ሸሻችኹ ፡ ትሸሻላችኹ ፤ አምላኬ ፡ እግዚአብሔርም ፡
ከቅዱሳኑ ፡ ዅሉ ፡ ጋራ ፡ ይመጣል ።

6 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ በረዶና ፡ ውርጭ ፡ እንጂ ፡ ብርሃን ፡ አይኾንም ።

7 ፤ አንድ ፡ ቀንም ፡ ይኾናል ፥ ርሱም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የታወቀ ፡ ይኾናል ፤ ቀንም ፡ አይኾንም ፥ ሌሊትም ፡
አይኾንም ፤ ሲመሽም ፡ ብርሃን ፡ ይኾናል ።

8 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ የሕይወት ፡ ውሃ ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ይወጣል ፤ እኩሌታው ፡ ወደምሥራቁ ፡ ባሕር ፥ እኩሌታውም ፡
ወደምዕራቡ ፡ ባሕር ፡ ይኼዳል ፤ ይህ ፡ በበጋና ፡ በክረምት ፡ ይኾናል ።

9 ፤ እግዚአብሔርም ፡ በምድር ፡ ዅሉ ፡ ላይ ፡ ይነግሣል ፤ በዚያ ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ አንድ ፥ ስሙም ፡ አንድ ፡
ይኾናል ።

10 ፤ ምድር ፡ ዅሉ ፡ ከጌባ ፡ ዠምሮ ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ ደቡብ ፡ በኩል ፡ እስካለችው ፡ እስከ ፡ ሬሞን ፡ ድረስ ፡ ተለውጣ ፡
እንደ ፡ ዐረባ ፡ ትኾናለች ፤ ርሷም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ትላለች ፥ ከብንያምም ፡ በር ፡ ዠምሮ ፡ እስከፊተኛው ፡ በር ፡ ስፍራ ፡
እስከማእዘኑ ፡ በር ፡ ድረስ ፥ ከሐናንኤልም ፡ ግንብ ፡ ዠምሮ ፡ እስከንጉሡ ፡ መጥመቂያ ፡ ድረስ ፡ በስፍራዋ ፡ ትኖራለች ።

11 ፤ ሰዎችም ፡ ይኖሩባታል ፥ ከዚያም ፡ ወዲያ ፡ ርግማን ፡ አይኾንም ፤ ኢየሩሳሌምም ፡ ተዘልላ ፡ ትኖራለች ።

12 ፤ እግዚአብሔርም ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ጋራ ፡ የተዋጉትን ፡ አሕዛብ ፡ ዅሉ ፡ የሚቀሥፍበት ፡ ቸነፈር ፡ ይህ ፡
ነው ፤ በእግራቸው ፡ ሲቆሙ ፡ ሥጋቸው ፡ ይበሰብሳል ፥ ዐይኖቻቸውም ፡ በዐይኑ ፡ ሥባቸው ፡ ውስጥ ፡
ይበሰብሳሉ ፥ ምላሳቸውም ፡ በአፋቸው ፡ ውስጥ ፡ ይበሰብሳል ።

13 ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ታላቅ ፡ ሽብር ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ይኾናል ፤ እያንዳንዱም ፡ የባልንጀራውን ፡
እጅ ፡ ይይዛል ፥ እጁም ፡ በባልንጀራው ፡ እጅ ፡ ላይ ፡ ይነሣል ።

14 ፤ ይሁዳም ፡ ደግሞ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ውስጥ ፡ ኾኖ ፡ ይዋጋል ፤ በዙሪያም ፡ ያሉት ፡ የአሕዛብ ፡ ዅሉ ፡ ሀብት ፡ እጅግ ፡
ብዙ ፡ ወርቅና ፡ ብር ፡ ልብስም ፡ ይሰበሰባል ።

15 ፤ በፈረስና ፡ በበቅሎ ፥ በግመልና ፡ በአህያ ፥ በዚያም ፡ ሰፈር ፡ ባለ ፡ እንስሳ ፡ ዅሉ ፡ ላይ ፡ የኾነ ፡ ቸነፈር ፡ እንደዚያ ፡
ያለ ፡ ቸነፈር ፡ ይኾናል ።

16 ፤ በኢየሩሳሌም ፡ ላይ ፡ ከመጡት ፡ ከአሕዛብ ፡ ዅሉ ፡ የቀሩት ፡ ዅሉ ፡ ለንጉሡ ፡ ለሰራዊት ፡ ጌታ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
ይሰግዱ ፡ ዘንድ ፥ የዳስ ፡ በዓልንም ፡ ያከብሩ ፡ ዘንድ ፡ በየዓመቱ ፡ ይወጣሉ ።

17 ፤ ከምድርም ፡ ወገኖች ፡ ዅሉ ፡ ለንጉሡ ፡ ለሰራዊት ፡ ጌታ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ይሰግዱ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡
ለማይወጡ ፡ ለእነርሱ ፡ ዝናብ ፡ አይዘንብላቸውም ።

18 ፤ የግብጽም ፡ ወገን ፡ ባይወጣ ፡ ወደዚያም ፡ ባይመጣ ፥ እግዚአብሔር ፡ የዳስ ፡ በዓልን ፡ ያከብሩ ፡ ዘንድ ፡
የማይወጡትን ፡ አሕዛብ ፡ የሚቀሥፍበት ፡ ቸነፈር ፡ በርሱ ፡ ላይ ፡ ይኾናል ።

19 ፤ የግብጽ ፡ ቅጣት ፥ የዳስ ፡ በዓልንም ፡ ያከብሩ ፡ ዘንድ ፡ የማይወጡት ፡ የአሕዛብ ፡ ዅሉ ፡ ቅጣት ፡ እንደዚህ ፡
ይኾናል ።

20 ፤ በዚያ ፡ ቀን ፡ በፈረሶች ፡ ሻኵራ ፡ ላይ ፦ ለእግዚአብሔር ፡ የተቀደሰ ፡ ተብሎ ፡ ይጻፋል ፤ በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡
ያሉ ፡ ምንቸቶች ፡ በመሠዊያው ፡ ፊት ፡ እንዳሉ ፡ ዳካዎች ፡ ይኾናሉ ።

21 ፤ በኢየሩሳሌምና ፡ በይሁዳ ፡ ያሉ ፡ ምንቸቶችም ፡ ዅሉ ፡ ለሰራዊት ፡ ጌታ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የተቀደሱ ፡
ይኾናሉ ፤ የሚሠዉትም ፡ ሰዎች ፡ ዅሉ ፡ ይመጣሉ ፡ ከነዚያም ፡ ወስደው ፡ ይቀቅሉባቸዋል ፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ በሰራዊት ፡
ጌታ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቤት ፡ ከነዓናዊው ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲያ ፡ አይገኝም ፨

# ትንቢተ ፡ ሚልክያስ ።

(ክለሳ.1.20020507)

___________________ትንቢተ ፡ ሚልክያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 1 ። __________________

## ምዕራፍ ፡ 1 ።

1 ፤ በሚልክያስ ፡ እጅ ፡ ለእስራኤል ፡ የኾነ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ሸክም ፡ ይህ ፡ ነው ።

2 ፤ ወድጃችኋለኹ ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ እናንተ ፡ ግን ፦ በምን ፡ ወደድኸን ፧ ብላችኋል ። ዔሳው ፡ የያዕቆብ ፡
ወንድም ፡ አልነበረምን ፧ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፤ ያዕቆብንም ፡ ወደድኹ ፥ ዔሳውንም ፡ ጠላኹ ፤

3 ፤ ተራራዎቹንም ፡ በረሓ ፡ አደረግኋቸው ፥ ርስቱንም ፡ ለምድረ ፡ በዳ ፡ ቀበሮዎች ፡ አሳልፌ ፡ ሰጠኋቸው ።

4 ፤ ኤዶምያስ ፦ እኛ ፡ ፈርሰናል ፥ ነገር ፡ ግን ፥ የፈረሰውን ፡ መልሰን ፡ እንሠራለን ፡ ቢል ፥ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ ይላል ፦ እነርሱ ፡ ይሠራሉ ፥ እኔ ፡ ግን ፡ አፈርሳለኹ ፤ በሰዎችም ፡ ዘንድ ፦ የበደል ፡ ዳርቻና ፡
እግዚአብሔር ፡ ለዘለዓለም ፡ የተቈጣው ፡ ሕዝብ ፡ ይባላል ።

5 ፤ ዐይኖቻችኹም ፡ ያያሉ ፥ እናንተም ፦ እግዚአብሔር ፡ ከእስራኤል ፡ ዳርቻ ፡ ወዲያ ፡ ታላቅ ፡ ይኹን ፡ ትላላችኹ ።

6 ፤ እናንተ ፡ ስሜን ፡ የምታቃልሉ ፡ ካህናት ፡ ሆይ ፥ ልጅ ፡ አባቱን ፥ ባሪያም ፡ ጌታውን ፡ ያከብራል ፤ እኔስ ፡ አባት ፡
ከኾንኹ ፡ ክብሬ ፡ ወዴት ፡ አለ ፧ ጌታስ ፡ ከኾንኹ ፡ መፈራቴ ፡ ወዴት ፡ አለ ፧ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔር ። እናንተም ፦ ስምኽን ፡ ያቃለልን ፡ በምንድር ፡ ነው ፧ ብላችኋል ።

7 ፤ በመሠዊያዬ ፡ ላይ ፡ ርኩስ ፡ እንጀራ ፡ ታቀርባላችኹ ። እናንተም ፦ ያረከስንኽ ፡ በምንድር ፡
ነው ፧ ብላችኋል ። የእግዚአብሔር ፡ ገበታ ፡ የተነቀፈ ፡ ነው ፡ በማለታችኹ ፡ ነው ።

8 ፤ ዕውር ፡ መሥዋዕትንም ፡ ስታቀርቡ ፡ ይህ ፡ ክፉ ፡ አይደለምን ፧ ዐንካሳውንና ፡ የታመመውን ፡ ስታቀርቡ ፡ ይህ ፡ ክፉ ፡
አይደለምን ፧ ያንን ፡ ለአለቃኽ ፡ አቅርብ ፤ በእውኑ ፡ ባንተ ፡ ደስ ፡ ይለዋልን ፧ ወይስ ፡ ፊትኽን ፡ ይቀበላልን ፧ ይላል ፡
የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

9 ፤ አኹንም ፡ ጸጋን ፡ ይሰጠን ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለምኑ ፤ ይህ ፡ ከእጃችኹ ፡ የተሰጠ ፡ሲኾን ፡ ከቶ ፡ ፊታችኹን ፡
ይቀበላልን ፧ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

10 ፤ በመሠዊያዬ ፡ ላይ ፡ እሳትን ፡ በከንቱ ፡ እንዳታቃጥሉ ፡ ከእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ደጅ ፡ የሚዘጋ ፡ ሰው ፡ ምነው ፡ በተገኘ!
በእናንተ ፡ ደስ ፡ አይለኝም ፥ ቍርባንንም ፡ ከእጃችኹ ፡ አልቀበልም ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

11 ፤ ከፀሐይ ፡ መውጫ ፡ ዠምሮ ፡ እስከ ፡ መግቢያዋ ፡ ድረስ ፡ ስሜ ፡ በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ ታላቅ ፡
ይኾናልና ፤ በየስፍራውም ፡ ለስሜ ፡ ዕጣን ፡ ያጥናሉ ፥ ንጹሕም ፡ ቍርባን ፡ ያቀርባሉ ፤ ስሜ ፡ በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ ታላቅ ፡
ይኾናልና ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

12 ፤ እናንተ ፡ ግን ፦ የእግዚአብሔር ፡ ገበታ ፡ ርኩስ ፡ ነው ፤ ፍሬውና ፡ መብሉም ፡ የተናቀ ፡ ነው ፡ በማለታችኹ ፡
አስነቀፋችኹት ።

13 ፤ እናንተ ፦ እንሆ ፥ ይህ ፡ ድካም ፡ ነው ፡ ብላችኹ ፡ ጢቅ ፡ አላችኹበት ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔር ፤ በቅሚያ ፡ የያዛችኹትንም ፡ ዐንካሳውንም ፡ የታመመውንም ፡ አቅርባችኋል ፤ እንዲሁ ፡ ቍርባንን ፡
ታመጣላችኹ ፤ በእውኑ ፡ ከእጃችኹ ፡ ይህን ፡ ልቀበለውን ፧ ይላል ፡ እግዚአብሔር ።

14 ፤ እኔ ፡ ታላቅ ፡ ንጉሥ ፡ ነኝና ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፥ ስሜም ፡ በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡ የተፈራ ፡
ነውና ፥ በመንጋው ፡ ውስጥ ፡ ተባት ፡ እያለው ፡ ለጌታ ፡ ተስሎ ፡ ነውረኛውን ፡ የሚሠዋ ፡ ሸንጋይ ፡ ሰው ፡ ርጉም ፡
ይኹን ።

___________________ትንቢተ ፡ ሚልክያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 2 ። __________________

ምዕራፍ ፡ 2 ።

1 ፤ አኹንም ፡ እናንተ ፡ ካህናት ፡ ሆይ ፥ ይህ ፡ ትእዛዝ ፡ ለእናንተ ፡ ነው ።

2 ፤ ለስሜ ፡ ክብር ፡ ትሰጡ ፡ ዘንድ ፡ ባትሰሙ ፥ በልባችኹም ፡ ባታደርጉት ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔር ፥ ርግማን ፡ እሰድባችኂለኹ ፥ በረከታችኹንም ፡ እረግማታለኹ ፤ አኹንም ፡ በልባችኹ ፡
አላደረጋችኹትምና ፡ እኔ ፡ ረግሜያታለኹ ።

3 ፤ እንሆ ፥ ክንዳችኹን ፡ እገሥጻለኹ ፥ የመሥዋዕታችኹንም ፡ ፋንድያ ፡ በፊታችኹ ፡ ላይ ፡ እበትናለኹ ፤ ከርሱም ፡
ጋራ ፡ በአንድነት ፡ ትወሰዳላችኹ ።

4 ፤ ቃል ፡ ኪዳኔ ፡ ከሌዊ ፡ ጋራ ፡ ይኾን ፡ ዘንድ ፡ ይህን ፡ ትእዛዝ ፡ እንደ ፡ ሰደድኹላችኹ ፡ ታውቃላችኹ ፥ ይላል ፡
የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

5 ፤ ቃል ፡ ኪዳኔ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ የሕይወትና ፡ የሰላም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ነበረ ፤ ይፈራ ፡ ዘንድም ፡ እነርሱን ፡
ሰጠኹት ፤ ርሱም ፡ ፈራኝ ፥ ከስሜም ፡ የተነሣ ፡ ደነገጠ ።

6 ፤ የእውነት ፡ ሕግ ፡ በአፉ ፡ ውስጥ ፡ ነበረች ፥ በከንፈሩም ፡ ውስጥ ፡ በደል ፡ አልተገኘበትም ፤ ከእኔም ፡ ጋራ ፡ በሰላምና ፡
በቅንነት ፡ ኼደ ፥ ብዙ ፡ ሰዎችንም ፡ ከኀጢአት ፡ መለሰ ።

7 ፤ ካህኑ ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መልእክተኛ ፡ ነውና ፥ ከንፈሮቹ ፡ ዕውቀትን ፡ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ፡
ይገባቸዋል ፥ ሰዎችም ፡ ሕግን ፡ ከአፉ ፡ ይፈልጉ ፡ ዘንድ ፡ ይገባቸዋል ።

8 ፤ እናንተ ፡ ግን ፡ ከመንገዱ ፡ ፈቀቅ ፡ ብላችኋል ፤ በሕግም ፡ ብዙ ፡ ሰዎችን ፡ አሰናክላችኋል ፤ የሌዊንም ፡ ቃል ፡
ኪዳን ፡ አስነውራችኋል ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

9 ፤ ስለዚህ ፥ መንገዴን ፡ እንዳልጠበቃችኹ ፥ በሕግም ፡ ለሰው ፡ ፊት ፡ እንዳዳላችኹ ፡ መጠን ፥ እኔ ፡ ደግሞ ፡ በሕዝብ ፡
ኹሉ ፡ ፊት ፡ የተናቃችኹና ፡ የተዋረዳችኹ ፡ አደርጌያችኋለኹ ።

10 ፤ ለኹላችን ፡ አንድ ፡ አባት ፡ ያለን ፡ አይደለምን ፧ አንድ ፡ አምላክስ ፡ የፈጠረን ፡ አይደለምን ፧ የአባቶቻችንን ፡ ቃል ፡
ኪዳን ፡ ለማስነቀፍ ፡ እኛ ፡ እያንዳንዳችን ፡ ወንድማችንን ፡ ስለ ፡ ምን ፡ አታለልን ፧

11 ፤ እግዚአብሔር ፡ የወደደውን ፡ መቅደስ ፡ ይሁዳ ፡ አርክሷልና ፥ የእንግዳውንም ፡ አምላክ ፡ ልጅ ፡ ሚስት ፡ አድርጎ ፡
አግብቷልና ፥ ይሁዳ ፡ አታሏል ፥ በእስራኤልና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ውስጥ ፡ ርኵሰት ፡ ተሠርቷል ።

12 ፤ ይህን ፡ ከሚያደርግ ፡ ሰው ፥ እግዚአብሔር ፡ የሚጠራውንና ፡ የሚመልሰውን ፡ ለሰራዊትም ፡ ጌታ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
ቍርባን ፡ የሚያቀርበውን ፡ ከያዕቆብ ፡ ድንኳን ፡ ያጠፋል ።

13 ፤ ይህንም ፡ ደግሞ ፡ አድርጋችኋል ፤ እግዚአብሔር ፡ ቍርባኑን ፡ ዳግመኛ ፡ እንዳይመለከት ፥ ከእጃችኹም ፡ በደስታ ፡
እንዳይቀበለው ፡ መሠዊያውን ፡ በእንባና ፡ በልቅሶ ፡ በሐዘንም ፡ ትከድናላችኹ ።

14 ፤ እናንተም ፦ ስለ ፡ ምንድር ፡ ነው ፧ ብላችኋል ። ሚስትኽ ፡ ባልንጀራኽና ፡ የቃል ፡ ኪዳንኽ ፡ ሚስት ፡ ኾና ፡ ሳለች ፡
ርሷን ፡ አታለኽታልና ፥ እግዚአብሔር ፡ በአንተና ፡ በልጅነት ፡ ሚስትኽ ፡ መካከል ፡ ምስክር ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ነው ።

15 ፤ እግዚአብሔር ፡ የሕይወትን ፡ መንፈስ ፡ አንድ ፡ አድርጎ ፡ ጠብቆልን ፡ የለምን ፧ ርሱም ፡ የሚፈልገው ፡ ምንድር ፡
ነው ፧ ዘር ፡ አይደለምን ፧ ስለዚህ ፡ መንፈሳችኹን ፡ ጠብቁ ፥ ማንም ፡ የልጅነት ፡ ሚስቱን ፡ አያታልል ።

16 ፤ መፋታትን ፡ እጠላለኹ ፥ ይላል ፡ የእስራኤል ፡ አምላክ ፡ እግዚአብሔር ፥ ልብሱንም ፡ በግፍ ፡ ሥራ ፡ የሚከድነውን ፡
ሰው ፡ እጠላለኹ ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ ስለዚህ ፥ እንዳታታልሉ ፡ መንፈሳችኹን ፡ ጠብቁ ።

17 ፤ እግዚአብሔርን ፡ በቃላችኹ ፡ አታክታችኋል ። እናንተም ፦ ያታከትነው ፡ በምንድር ፡ ነው ፧ ብላችኋል ። ክፉን ፡
የሚያደርግ ፡ ኹሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ መልካም ፡ ነው ፥ ርሱም ፡ በእነርሱ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፤ ወይስ ። የፍርድ ፡
አምላክ ፡ ወዴት ፡ አለ ፧ በማለታችኹ ፡ ነው ።

________________ትንቢተ ፡ ሚልክያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 3 ። ________________

ምዕራፍ ፡ 3 ።

1 ፤ እንሆ ፥ መልእክተኛዬን ፡ እልካለኹ ፥ መንገድንም ፡ በፊቴ ፡ ያስተካክላል ፤ እናንተም ፡ የምትፈልጉት ፡ ጌታ ፡
በድንገት ፡ ወደ ፡ መቅደሱ ፡ ይመጣል ፤ የምትወዱትም ፡ የቃል ፡ ኪዳን ፡ መልእክተኛ ፥ እንሆ ፥ ይመጣል ፥ ይላል ፡
የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

2 ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ርሱ ፡ እንደ ፡ አንጥረኛ ፡ እሳትና ፡ እንደ ፡ ዐጣቢ ፡ ሳሙና ፡ ነውና ፥ የሚመጣበትን ፡ ቀን ፡ መታገሥ ፡
የሚችል ፡ ማን ፡ ነው ፧ ርሱስ ፡ በተገለጠ ፡ ጊዜ ፡ የሚቆም ፡ ማን ፡ ነው ፧

3 ፤ ርሱም ፡ ብርን ፡ እንደሚያነጥርና ፡ እንደሚያጠራ ፡ ሰው ፡ ይቀመጣል ፥ የሌዊንም ፡ ልጆች ፡ ያጠራል ፥ እንደ ፡
ወርቅና ፡ እንደ ፡ ብርም ፡ ያነጥራቸዋል ፤ እነርሱም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በጽድቅ ፡ ቍርባንን ፡ የሚያቀርቡ ፡ ይኾናሉ ።

4 ፤ እግዚአብሔርም ፡ እንደ ፡ ዱሮው ፡ ዘመንና ፡ እንደ ፡ ቀደሙት ፡ ዓመታት ፡ በይሁዳና ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ቍርባን ፡
ደስ ፡ ይለዋል ።

5 ፤ ለፍርድ ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ እቀርባለኹ ፤ በመተተኛዎችና ፡ በአመንዝራዎች ፥ በሐሰትም ፡ በሚምሉ ፥ የምንደኛውን ፡
ደመ ፡ ወዝ ፡ በሚከለክሉ ፥ መበለቲቱንና ፡ ድኻ ፡ አደጉን ፡ በሚያስጨንቁ ፥ የመጻተኛውንም ፡ ፍርድ ፡
በሚያጣምሙ ፥ እኔንም ፡ በማይፈሩ ፡ ላይ ፡ ፈጣን ፡ ምስክር ፡ እኾንባቸዋለኹ ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

6 ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ አልለወጥም ፤ እናንተ ፡ የያዕቆብ ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፥ ስለዚህ ፡ የጠፋችኹ ፡ አይደላችኹም ።

7 ፤ ከአባቶቻችኹ ፡ ዘመን ፡ ዠምሮ ፡ ከሥርዐቴ ፡ ፈቀቅ ፡ ብላችኊል ፥ ርሷንም ፡ አልጠበቃችኹም ፦ ወደ ፡ እኔ ፡
ተመለሱ ፥ እኔም ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ እመለሳለኹ ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ። እናንተ ፡
ግን ፦ የምንመለሰው ፡ በምንድር ፡ ነው ፧ ብላችኊል ።

8 ፤ ሰው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ይሰርቃልን ፧ እናንተ ፡ ግን ፡ እኔን ፡ ሰርቃችኊል ። እናንተም ፦ የሰረቅንኽ ፡ በምንድር ፡
ነው ፧ ብላችኊል ። በዓሥራትና ፡ በበኵራት ፡ ነው ።

9 ፤ እናንተ ፥ ይህ ፡ ሕዝብ ፡ ኹሉ ፥ እኔን ፡ ሰርቃችኊልና ፥ በርግማን ፡ ርጉሞች ፡ ናችኹ ።

10 ፤ በቤቴ ፡ ውስጥ ፡ መብል ፡ እንዲኾን ፡ ዓሥራቱን ፡ ኹሉ ፡ ወደ ፡ ጐተራ ፡ አግቡ ፤ የሰማይንም ፡ መስኮት ፡
ባልከፍትላችኹ ፥ በረከትንም ፡ አትረፍርፌ ፡ ባላፈስላችኹ ፡ በዚህ ፡ ፈትኑኝ ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

11 ፤ ስለ ፡ እናንተ ፡ ነቀዙን ፡ እገሥጻለኹ ፥ የምድራችኹንም ፡ ፍሬ ፡ አያጠፋም ፤ በዕርሻችኹም ፡ ያለው ፡ ወይን ፡
ፍሬውን ፡ አያረግፍም ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

12 ፤ የተድላ ፡ ምድር ፡ ትኾናላችኹና ፡ አሕዛብ ፡ ኹሉ ፡ ብፁዓን ፡ ብለው ፡ ይጠሯችኊል ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔር ።

13 ፤ ቃላችኹ ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ድፍረት ፡ ኾኗል ፥ ይላል ፡ እግዚአብሔር ። እናንተ ፡ ግን ፦ ባንተ ፡ ላይ ፡ ደፍረን ፡
የተናገርነው ፡ በምንድር ፡ ነው ፧ ብላችኊል ።

14 ፤ እናንተም ፦ እግዚአብሔርን ፡ ማገልገል ፡ ከንቱ ፡ ነው ፤ ትእዛዙንስ ፡ በመጠበቅ ፥ በሰራዊት ፡ ጌታ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ሐዘንተኛዎች ፡ ኾነን ፡ በመኼድ ፡ ምን ፡ ይረባናል ፧

15 ፤ አኹንም ፡ የሚታበዩትን ፡ ሰዎች ፡ ብፁዓን ፡ ብለን ፡ እንጠራቸዋለን ፤ ክፉንም ፡ የሚሠሩ ፡ ጸንተዋል ፡
እግዚአብሔርንም ፡ ይፈታተናሉ ፥ ያመልጣሉም ፡ ብላችኊል ።

16 ፤ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈሩ ፡ ርስ ፡ በርሳቸው ፡ ተነጋገሩ ፤ እግዚአብሔርም ፡
አደመጠ ፥ ሰማም ፥ እግዚአብሔርንም ፡ ለሚፈሩ ፡ ስሙንም ፡ ለሚያስቡ ፡ የመታሰቢያ ፡ መጽሐፍ ፡ በፊቱ ፡ ተጻፈ ።

17 ፤ እኔ ፡ በምሠራበት ፡ ቀን ፡ እነርሱ ፡ የእኔ ፡ ገንዘብ ፡ ይኾናሉ ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፤ ሰውም ፡
የሚያገለግለውን ፡ ልጁን ፡ እንደሚምር ፥ እንዲሁ ፡ እምራቸዋለኹ ።

18 ፤ ተመልሳችኹም ፡ በጻድቁና ፡ በኀጢአተኛው ፡ መካከል ፥ ለእግዚአብሔር ፡ በሚገዛውና ፡ በማይገዛው ፡ መካከል ፡
ትለያላችኹ ።

__________________ትንቢተ ፡ ሚልክያስ ፥ ምዕራፍ ፡ 4 ። __________________

ምዕራፍ ፡ 4 ።

1 ፤ እንሆ ፥ እንደ ፡ ምድጃ ፡ እሳት ፡ የሚነድ ፡ ቀን ፡ ይመጣል ፤ ትዕቢተኛዎችና ፡ ኀጢአትን ፡ የሚሠሩ ፡ ኹሉ ፡ ገለባ ፡
ይኾናሉ ፤ የሚመጣውም ፡ ቀን ፡ ያቃጥላቸዋል ፥ ሥርንና ፡ ቅርንጫፍንም ፡ አይተውላቸውም ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡
እግዚአብሔር ።

2 ፤ ነገር ፡ ግን ፥ ስሜን ፡ ለምትፈሩት ፡ ለእናንተ ፡ የጽድቅ ፡ ፀሓይ ፡ ትወጣላችኋለች ፥ ፈውስም ፡ በክንፎቿ ፡ ውስጥ ፡
ይኾናል ፤ እናንተም ፡ ትወጣላችኹ ፥ እንደ ፡ ሰባም ፡ እንቦሳ ፡ ትፈነጫላችኹ ።

3 ፤ በምሠራበት ፡ ቀን ፡ በደለኛዎች ፡ ከእግራችኹ ፡ ጫማ ፡ በታች ፡ ዐመድ ፡ ይኾናሉና ፡ እናንተ ፡
ትረግጧቸዋላችኹ ፥ ይላል ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ።

4 ፤ ለእስራኤል ፡ ኹሉ ፡ ሥርዐትንና ፡ ፍርድን ፡ አድርጌ ፡ በኰሬብ ፡ ያዘዝኹትን ፡ የባሪያዬን ፡ የሙሴን ፡ ሕግ ፡ ዐስቡ ።

5 ፤ እንሆ ፥ ታላቁና ፡ የሚያስፈራው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቀን ፡ ሳይመጣ ፡ ነቢዩን ፡ ኤልያስን ፡ እልክላችኋለኹ ።

6 ፤ መጥቼም ፡ ምድርን ፡ በርግማን ፡ እንዳልመታ ፡ ርሱ ፡ የአባቶችን ፡ ልብ ፡ ወደ ፡ ልጆች ፥ የልጆችንም ፡ ልብ ፡ ወደ ፡
አባቶች ፡ ይመልሳል ፨

# መጽሐፈ ፡ ዕዝራ ፡ ሱቱኤል ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ አገራችን ፡ ኢየሩሳሌም ፡ በጠፋች ፡ በሠላሳ ፡
ዘመን ፡ ዕዝራ ፡ እባል ፡ የነበርኩ ፡ እኔ ፡ ሱቱ
ኤል ፡ በባቢሎን ፡ ነበርኩ ፡ በምኝታዬም ፡ እኔ ፡
ተኝቼ ፡ ነበር ፡ ፊቴ ፡ ግን ፡ ተገልጦ ፡ ነበር ፡ በል
ቡናዬም ፡ አሳብ ፡ ይወጣ ፡ ይወርድ ፡ ነበር ።
፪፤ የኢየሩሳሌምን ፡ ጥፋቷን ፡ አይቻለሁና ፡ በባቢ
ሎን ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎችን ፡ ተድላ ፡ ደስታንም ፡
አይቻለሁና ።
፫፤ ፈጽማ ፡ ሰውነቴ ፡ ታወከች ፡ የሚያስፈራ ፡ ነገር
ንም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጋራ ፡ እናገር ፡ ጀመርኩ ።
፬፤ አቤቱ ፡ ስናገር ፡ እንዲህ ፡ አልኩ ፡ አስቀድሞ ፡
ምድርን ፡ በፈጠርካት ፡ ጊዜ ፡ አንተ ፡ እንዲህ ፡
ያልክ ፡ አይደለምን ፡ አዳምን ፡ በፈራሽ ፡ ሥጋ ፡
ታስገኘው ፡ ዘንድ ፡ ይኸንን ፡ ብቻህን ፡ መሬ
ትን ፡ ያዘዝካት ፡ አይደለምን ።
፭፤ አዳምም ፡ የሥልጣንህ ፡ ፍጥረት ፡ ነው ፡ ነባ
ቢት ፡ ነፍስን ፡ አዋህደህ ፡ ፈጠርከው ፡ በነባ
ቢት ፡ ነፍስም ፡ በፊትህ ፡ ደህነኛ ፡ ሆኖ ፡ ኖረ ።
፮፤ ምድር ፡ ተፈጥራ ፡ ሳትጸና ፡ ሥልጣንህ ፡ ወደ
ፈጠረቻት ፡ ወደ ፡ ገነትም ፡ አገባኸው ።
፯፤ ዕፀ ፡ በለስን ፡ አትብላ ፡ ብለህ ፡ አዘዝከው ፡ እሱ ፡
ግን ፡ ትእዛዝክን ፡ አፈረሰ ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በሱ ፡
በልጆቹ ፡ በልጅ ፡ ልጆቹም ፡ ላይ ፡ ሞትን ፡ አመ
ጣህ ፡ አሕዛቡም ፡ ሕዝቡም ፡ ነገደ ፡ ያፌት ፡ ነገደ ፡
ሴምም ፡ ቍጥር ፡ የሌላቸው ፡ መንደር ፡ መንድ
ረው ፡ የሚኖሩትም ፡ ከሱ ፡ ተወለዱ ።

አሕዛብም ፡ ሁሉ ፡ በሥራቸው ፡ ፀንተው ፡ኖሩ ። ፰፤
በፊትህ ፡ በደሉ ፡ አንተንም ፡ ከዱ ፡ አንተ ፡ ግን ፡
አልከለከልካቸውም ።
ዳግመኛም ፡ በጊዜው ፡ ጊዜ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ፱፤
በሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ላይና ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ የጥ
ፋት ፡ ውሀን ፡ አመጣህ ፡ አጠፋሃቸው ።
ቅጣታቸውም ፡ የተካከለ ፡ ሆነ ፡ በአዳም ፡ ላይ ፡ ፲፤
ሞትን ፡ እንዳመጣህ ፡ እንደዚሁ ፡ በእሊህም ፡
ላይ ፡ የጥፋት ፡ ውሀን ፡ አመጣህ ።
ከነሳቸውም ፡ ስሙ ፡ ኖኅ ፡ የሚባል ፡ አንድ ፡ ፲፩፤
ሰውን ፡ ከቤተ ፡ ሰቡ ፡ ጋራ ፡ አስቀረህ ፡ ከሱም ፡
ኃጥአንና ፡ ጻድቃን ፡ ሁሉ ፡ ተወለዱ ።
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ይበዙ ፡ ዘንድ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ፲፪፤
የሚኖሩትም ፡ ምድርንም ፡ ይመሏት ፡ ዘንድ ፡
በጀመሩ ፡ ጊዜ ፡ ልጆቻቸውም ፡ በበዙ ፡ ጊዜ ፡
ከነሳቸው ፡ ብዙ ፡ የሚሆኑ ፡ ሕዝቡም ፡ አሕዛ
ቡም ፡ በተወለዱ ፡ ጊዜ ፡ ከቀደመው ፡ በደል ፡
ይልቅ ፡ ዳግመኛ ፡ እጅግ ፡ ይበድሉ ፡ ጀመሩ ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በፊትህም ፡ በበደሉ ፡ ጊዜ ፡ ከነ ፲፫፤
ሳቸው ፡ ስሙ ፡ አብርሃም ፡ የሚባል ፡ አንድ ፡
ሰው ፡ መረጥህ ።
ወደድኸው ፡ የዘመኑንም ፡ መጨረሻ ፡ ለብቻው ፡ ፲፬፤
በሌሊት ፡ አሳየኸው ።
ልጆቹን ፡ ዓለም ፡ እስኪያልፍ ፡ ድረስ ፡ ፈጽ ፲፭፤
መህ ፡ እንዳታጠፋቸው ፡ ለዘላለሙ ፡ መሐላ
ውን ፡ አጸናህለት ።
ከግብፅ ፡ የወጡ ፡ ወደ ፡ ደብረ ፡ ሲናም ፡ የወሰ ፲፮፤
ድካቸውን ።

፲፯፡ ሰማያትን ፡ ዝቅ ፡ ያደረግህላቸውን ፡ ምድርንም ፡
ያንቀወጥህላቸውን ፡ ግብፅንም ፡ ያጠፋህላቸ
ውን ፡ ጥልቅ ፡ ውሀውንም ፡ ያንቀወጥህላቸውን ፡
በሕፋንም ፡ ያንቀወጥህላቸውን ፡ ልጆችን ፡
ዓለም ፡ እስኪያልፍ ፡ ድረስ ፡ ፈጽመህ ፡ እንዳታ
ጠፋቸው ፡ ለዘላለሙ ፡ መሐላውን ፡ አጸናህላ
ቸው ።
፲፰፡ ለእስራኤል ፡ ወገንና ፡ ለያዕቆብ ፡ ልጆች ፡ አታ
ምልክንና ፡ ዘጠኙን ፡ ሕጊጋት ፡ ትሰጣቸው ፡
ዘንድ ፡ ንውጽውጽታና ፡ እሳት ፡ በረድና ፡
ነፋስ ፡ የሚሆኑ ፡ አራቱ ፡ የጌትነትህ ፡ ታምራ
ቶችህ ፡ ተደረጉ ።
፲፱፡ ነገር ፡ ግን ፡ የቀደመ ፡ ሰው ፡ አዳም ፡ ፈታዊ ፡
ልቡናን ፡ ገንዘብ ፡ አድርጎ ፡ ነበርና ፡ በነሱ ፡
የሕግህ ፡ ሥራ ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ ከነሱ ፡ ክፉ ፡
አሳብን ፡ አላራቅህም ።
፳፡ ድል ፡ ተነሣ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ከሱ ፡ የተወለዱ ፡ ልጆ
ችም ፡ ሁሉ ፡ ድል ፡ ተነሡ ፡ እንጂ ፡ ድል ፡ የተ
ነሣ ፡ እሱ ፡ ብቻ ፡ አይደለም ።
፳፩፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ከሕግህ ፡ ጋራ ፡ ያቺ ፡ ኃጢአት ፡
ከሰኑ ፡ ክህደት ፡ ጋራ ፡ በሰው ፡ ሁሉ ፡ ልቡና ፡
ፀንታ ፡ ኖረች ፡ እውነት ፡ ነገርም ፡ ጠፋች ፡
ሐሰት ፡ ግን ፡ ፀንታ ፡ ኖረች ።
፳፪፡ ዘመን ፡ አበው ፡ አለፈ ፡ ዘመን ፡ መሳፍንትም ፡
ተጨረሰ ፡ ስሙ ፡ ዳዊት ፡ የሚባል ፡ አገልጋይ
ህን ፡ ለመንግሥት ፡ አስነሣህ ።
፳፫፡ ስምህ ፡ ሊመሰገንበት ፡ መሥዋዕትህን ፡ ሊሠ
ዋበት ፡ ቤተ ፡ መቅደስን ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ ሥራ ፡
አልከው ።
፳፬፡ ዘመን ፡ ነገሥት ፡ ብዙ ፡ ሆነ ፡ ምንም ፡ ምን ፡ የሚ
ሠሩት ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ ቢኖር ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡
የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ በደሉ ።
፳፭፡ ፈታዊ ፡ ልቡናን ፡ ገንዘብ ፡ አድርገውታልና ፡
አዳም ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ እንደ ፡ ሠራ ፡ ልጆቹም ፡
ሁሉ ፡ በደሉ ።
፳፮፡ አገርህ ፡ ኢየሩሳሌምንም ፡ በጠላቶችህ ፡ በባቢ
ሎን ፡ ሰዎች ፡ እጅ ፡ አሳልፈህ ፡ ሰጠህ ።
፳፯፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ በልቡናዬ ፡ ጸዮን ፡ የምትባል ፡
ሀገርን ፡ እጅ ፡ ያደረጋት ፡ ዘንድ ፡ በባቢሎን ፡
የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ እውነት ፡ ሥራን ፡ በመሥ
ራት ፡ በውኑ ፡ ይበልጡናልን ፡ አልኩ ።
፳፰፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ባቢሎን ፡ በደረስሁ ፡ ጊዜ ፡
ቍጥር ፡ የሌለው ፡ ብዙ ፡ ኃጢአት ፡ ሲሠራ ፡
አየሁ ፡ ሰውነቴም ፡ ብዙ ፡ የሆኑ ፡ ከዓተኞችን ፡
አየች ፡ እነሆ ፡ ኃጢአቱም ፡ ሲሠራ ፡ ሠላሳ ፡
ዘመን ፡ ነው ፡ ኃጢአቱም ፡ በመሠራቱ ፡ ልቡ
ናዬ ፡ አደነቀ ።
፳፱፡ የባቢሎንን ፡ ሰዎች ፡ እንድትታገሳቸው ፡ አይቼ ፡
ሕግንም ፡ የዘነጉትን ፡ ሰዎች ፡ እንድትራራላ
ቸው ፡ ወገኖችህን ፡ ትተህ ፡ ጠላቶችህን ፡ እን
ድትጠብቅ ፡ አይቼ ፡ ልቡናዬ ፡ አደነቀ ።
፴፡ የማንንም ፡ ኃጢአት ፡ አልተመለከትህም ፡
የዚች ፡ ሥራ ፡ ፍጻሜዋ ፡ እንደምን ፡ ነው ፡ እው
ነት ፡ ሥራ ፡ በመሥራት ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ባቢ
ሎን ፡ የምትበልጠው ፡ ሙብስጥ ፡ አለን ።
ከእስራኤል ፡ ሌላ ፡ ወገን ፡ ያወቀህ ፡ አለን ፡ ፴፩፡
ወይስ ፡ በሕግህ ፡ እንደ ፡ ያዕቆብ ፡ የታመነ ፡
ሌላ ፡ ወገን ፡ አለን ።
ዋጋው ፡ ያልተገለጸ ፡ ድካሙ ፡ ዋጋውን ፡ ያላ ፴፪፡
ሰጠው ፡ እንደ ፡ ያዕቆብ ፡ ሌላ ፡ ወገን ፡ አለን ፡
ወደ ፡ አሕዛብም ፡ በሄድሁ ፡ ጊዜ ፡ ሕግህን ፡ ትእ
ዛዝህን ፡ ሳይሠሩ ፡ ደስ ፡ ብሏቸው ፡ አገኘኋ
ቸው ።
አሁንም ፡ በባቢሎን ፡ ሰዎች ፡ ኃጢአት ፡ ዘንድ ፡ ፴፫፡
የኛ ፡ ኃጢአት ፡ የሚዛን ፡ ውልብልቢትን ፡ የም
ትመስል ፡ የሰናፍጭ ፡ ቅንጣት ፡ ያህል ፡ በልጦ ፡
ይገኝ ፡ እንደሁ ፡ በባቢሎን ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡
ኃጢአትና ፡ የኛን ፡ ኃጢአት ፡ በሚዛን ፡ መዝን ።
ወዲያው ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ፴፬፡
በፊትህ ፡ ያልበደሉ ፡ መቼ ፡ ነው ፡ ወይስ ፡ ሕግ
ህን ፡ እንደዚህ ፡ የጠበቀ ፡ ወገን ፡ ማነው ።
ሕግህን ፡ ፈጽሞ ፡ የጠበቀ ፡ ወገንስ ፡ በዚህ ፡ ፴፭፡
ዓለም ፡ አይገኝም ።

ምዕራፍ ፡ ፪ ።

ስሙ ፡ ዑርኤል ፡ የሚባል ፡ መልአክ ፡ ወደኔ ፡ ፩፡
የተላከ ፡ ይህ ፡ መልአክ ፡ መለሰልኝ ።
የልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡ የጌትነቱን ፡ ፍርድ ፡ ፪፡
መርምረህ ፡ ታውቅ ፡ ዘንድ ፡ ልቡናህ ፡ አደነ
ቀን ።
አዎን ፡ ጌታዬ ፡ አልሁት ፡ ሦስቱን ፡ ሥራዎች ፡ ፫፡
እገልጥልህ ፡ ዘንድ ፡ ሦስቱንም ፡ ምሳሌዎች ፡
በፊትህ ፡ እኖር ፡ ዘንድ ፡ ተላክሁ ፡ አለኝ ።
ከሦስቱ ፡ ምሳሌ ፡ አንዲቱ ፡ የነገርኸኝ ፡ እንደ ፡ ፬፡
ሆነ ፡ እኔም ፡ ታውቀው ፡ ዘንድ ፡ የምትወዳትን ፡
ይህችን ፡ ሥራ ፡ እነግርሃለሁ ፡ ይህ ፡ ፈታዊ ፡
ልቡና ፡ ስለምንም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አስተምርሃለሁ ።
አቤቱ ፡ በል ፡ ተናገር ፡ አልሁት ፡ እሳቱን ፡ በሚ ፭፡
ዛን ፡ መዝነህ ፡ ነፋሱንም ፡ በላዳን ፡ ሰፍረህ ፡ አሳ
የኝ ፡ ( በባሕርያቸው ፡ አይሰፈሩምና ፡ ) ትላ
ንት ፡ ያለፈችውንም ፡ ቀን ፡ እንደ ፡ ዛሬ ፡ አድር
ገህ ፡ አሳየኝ ፡ አለኝ ።
ስለዚህ ፡ ነገር ፡ እኔን ፡ እንደ ፡ ጠየቅኸኝ ፡ ይህን ፡ ፮፡
ነገር ፡ ማድረግ ፡ የሚችለው ፡ ከሴቶች ፡ የተወ
ለደ ፡ ሰው ፡ ማነው ፡ አልሁት ።
በባሕር ፡ ውስጥ ፡ ምን ፡ ያህል ፡ ቤቶች ፡ አሉ ፡ ፯፡
ብዬ ፡ ጠይቄህስ ፡ ቢሆን ፡ በጥልቅ ፡ ባሕርስ ፡
ውስጥ ፡ ምን ፡ ያህል ፡ ፈሳሾች ፡ አሉ ፡ በሰማ
ይስ ፡ ምን ፡ ያህል ፡ ጎዳና ፡ አለ ፡ የሲኦልስ ፡ ጎዳና ፡
በየት ፡ ነው ፡ ወይስ ፡ የገነት ፡ ጎዳና ፡ በየት ፡ ነው ፡
ብዬ ፡ ጠይቄህስ ፡ ቢሆን ።
ወደ ፡ ጥልቅ ፡ ባሕር ፡ አልወረድሁም ፡ ወደ ፡ ፰፡
ሲኦልም ፡ ፈጽሜ ፡ አልወረድሁም ፡ ወደ ፡ ሰማ
ይም ፡ አልመጣሁም ፡ ብትለኝ ፡ የተገባ ፡ ነበር ።
የእሳትና ፡ የነፋስን ፡ ያለፈችውን ፡ ቀን ፡ ነገር ፡ ፱፡
ጠየቅሁህ ፡ እንጂ ፡ አሁን ፡ ግን ፡ ይኸን ፡ አል
ጠየቅሁህም ፡ እነሆ ፡ ማወቅን ፡ አትችልም ፡
የነዚህን ፡ ነገር ፡ የመለስክልኝ ፡ የለም ፡ አለኝ ፡

አለ ።
፲፤ በባሕርይህ ፡ ያለውን ፡ ማወቅ ፡ አልተቻለህ ።
፲፩፤ የልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡ ፍርዱ ፡ ባለመመር
መር ፡ ተወስኗልና ፡ የእግዚአብሔር ፡ የፍርዱን ፡
ምሥጢር ፡ ማወቅ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ይቻልሃል ፡
የምትፈርስ ፡ የምትበሰብስ ፡ አንተ ፡ የማይፈ
ርስ ፡ የማይበሰብስ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ፍርዱን ፡
ማወቅ ፡ አትችልም ።
፲፪፤ ይህን ፡ በሰማሁም ፡ ጊዜ ፡ በግምባሬ ፡ ፍግም ፡
ብዬ ፡ ወደቅሁ ፡ ስንፈጠር ፡ ተፈጥረን ፡ በኃጢ
አት ፡ ስንኖር ፡ መከራ ፡ ስንቀበል ፡ ባልተፈጠ
ርን ፡ ባልተሻለን ፡ ነበር ፡ መከራ ፡ እንድንቀበል ፡
እናውቅም ፡ አልሁ ።
፲፫፤ ታላላቁ ፡ ታናናሹም ፡ ዛፍ ፡ ሄደው ፡ ምክርን ፡
ተማከሩ ።
፲፬፤ ከፊታችን ፡ እናርቃት ፡ ዘንድ ፡ ኑ ፡ ሂደን ፡ ባሕ
ርን ፡ እንውጋት ፡ ባሕርን ፡ ወግተን ፡ ለዛፎነታ
ችን ፡ ሌላ ፡ አገር ፡ እናቅና ፡ አሉ ።
፲፭፤ እንደ ፡ ዕፀው ፡ የባሕር ፡ ማዕበላትም ፡ ምክርን ፡
መከሩ ፡ ለማዕበልነታችን ፡ ሌላ ፡ ሀገር ፡ እና
ቀና ፡ ዘንድ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ያለ ፡ ዛፍን ፡ እን
ወጋው ፡ ዘንድ ፡ ኑ ፡ እንገዝመት ፡ አሉ ።
፲፮፤ እሳት ፡ ወጥታ ፡ በልታቸዋለችና ፡ የዛፍ ፡ ምክሩ ፡
ከንቱ ፡ ሆነ ።]
፲፯፤ አሸዋው ፡ ገድቦ ፡ ይዞታልና ፡ የባሕር ፡ ማዕበ
ልም ፡ ምክሩ ፡ እንደ ፡ ዛፍ ፡ ምክር ፡ ከንቱ ፡ ሆነ ።
፲፰፤ ፍርድ ፡ የምታውቅ ፡ ከሆነ ፡ ከነዚህ ፡ ማንን ፡
እውነተኛ ፡ ማንን ፡ ሐሰተኛ ፡ ታደርጋለህ ፡
አለኝ ።
፲፱፤ የብስ ፡ ለዛፍ ፡ ባሕር ፡ ለማዕበል ፡ ተሰጥታለችና ፡
ሁለቱም ፡ ፈራሽ ፡ ነገር ፡ አሰቡ ፡ አልሁት ።
፳፤ እውነት ፡ ነገር ፡ ፈርደህ ፡ እንደዚህ ፡ ለራስህ ፡
ለምን ፡ አትፈርድ ፡ ብሎ ፡ መለሰልኝ ።
፳፩፤ የብስ ፡ ለዛፍ ፡ ባሕር ፡ ለማዕበል ፡ እንደ ፡ ተሰ
ጠች ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎችም ፡
በዚህ ፡ ዓለም ፡ የሚደረገውን ፡ ምሥጢር ፡
ማወቅ ፡ ይችላሉ ፡ እንጂ ፡ የመላእክትን ፡ ምሥ
ጢር ፡ የእግዚአብሔር ፡ የጌትነቱን ፡ ፍርድ ፡
ማወቅ ፡ አይችሉም ፡ አለኝ ።
፳፪፤ አቤቱ ፡ እጠይቅሃለሁ ፡ ማወቅ ፡ የማይገባን ፡
ከሆነ ፡ በምናውቀው ፡ ግንዛብ ፡ እንግዲያ ፡ ልብ ፡
ለምን ፡ ተሰጠን ፡ ብዬ ፡ መለስኩለት ።
፳፫፤ እስራኤል ፡ ለአሕዛብ ፡ ተሰጥቷልና ፡ የወደድ
ከውም ፡ ወገን ፡ ለኃጢአተኞች ፡ ወገን ፡ ተሰ
ጥቷልና ፡ ያበቶቻችንም ፡ ኦሪት ፡ ጠፍታለ
ችና ፡ በውስጧም ፡ የተጻፈ ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡
የለምና ፡ ሁልጊዜ ፡ በኛ ፡ ላይ ፡ የሚመጣውን ፡
መከራ ፡ እመረምር ፡ ዘንድ ፡ ወደድሁ ፡ እንጂ ፡
እኔ ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፍርድ ፡ እመረ
ምር ፡ ዘንድ ፡ አልወደድሁም ።
፳፬፤ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ እንደ ፡ አንበጣ ፡ ፈጥነን ፡ እን
ሄዳለንና ፡ እነዋወራችንም ፡ እንደ ፡ ጢስ ፡
ነውና ፡ ሁልጊዜ ፡ በኛ ፡ ላይ ፡ የሚመጣውን ፡
መከራ ፡ እመረምር ፡ ዘንድ ፡ ወደድሁ ፡ እንጂ ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ፍርድ ፡ እመረምር ፡ ዘንድ ፡
አልወደድሁም ፡ እንዳናውቅ ፡ እናውቃለንና ፡
በሕሪውን ፡ አትመርምሩ ፡ ብለው ፡ ሊያስተም
ሩን ፡ አይገባም ።
ነገር ፡ ግን ፡ በኛ ፡ ስለ ፡ ተጠራ ፡ ስለ ፡ ክቡር ፡ ፳፭፤
ስሙ ፡ ምን ፡ እናደርጋለን ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ጠየ
ቅሁህ ፡ አልሁት ።
መለሰልኝ ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፡ በትሞት ፡ ታየዋ ፡ ፳፮፤
ለህ ፡ በሕይወት ፡ ብትኖር ፡ በጊዜው ፡ ጊዜ ፡
ታውቀዋለህ ።
ጭንቅን ፡ ደዌን ፡ የተመላ ፡ ይህ ፡ ዓለም ፡ የጻ ፳፯፤
ድቃንን ፡ ዋጋ ፡ ማስቀረት ፡ የማይቻለው ፡ ስለ
ሆነ ፡ ይህ ፡ ዓለም ፡ ያልፍ ፡ ዘንድ ፡ ይቸኩላልና ።
ስለሷ ፡ የጠየቅኸኝ ፡ ኃጢአት ፡ በዓለም ፡ ተዘር ፳፰፤
ታለችና ፡ መከራዋ ፡ ምጽዓትም ፡ አልደረሰምና ።
በርሻው ፡ ውስጥ ፡ የተዘራው ፡ መከር ፡ ካልታ ፳፱፤
ጨደ ፡ አዝመራው ፡ ካልተነሣ ፡ የተዘራበት ፡
በታው ፡ ርቆ ፡ እንዳይታይ ፡ ኃጢአት ፡ የተሠ
ራችበት ፡ ይህ ፡ ዓለምም ፡ ካላለፈ ፡ ኃጢአት ፡
ከሰው ፡ ርቆ ፡ አይታይም ።
ጥንቱን ፡ ኃጢአት ፡ በአዳም ፡ ልቡና ፡ ተሠርቶ ፡ ፴፤
ነበርና ፡ የኃጢአት ፡ ፍሬ ፡ ፍዳም ፡ በዝቷልና ፡
ይህ ፡ ኃጢአቱም ፡ ሲሠራ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡
ደርሷልና ፡ መከሩም ፡ ምጽዓትም ፡ እስኪደረስ ፡
ድረስ ፡ ሰውም ፡ ሲወለድ ፡ ኃጢአቱም ፡ ሲሠራ ፡
ይኖራልና ፡ አንተ ፡ ራስህ ፡ እስኪ ፡ አስበው ።
ቀድሞ ፡ ጥቂት ፡ ኃጢአት ፡ ቢሠራ ፡ ይህን ፡ ፴፩፤
ያህል ፡ የኃጢአት ፡ ፍዳ ፡ የበዛች ።
ጥቂት ፡ በጎ ፡ ሥራስ ፡ ቢሠራ ፡ ፍጻሜ ፡ የሌ ፴፪፤
ለው ፡ ብዙ ፡ ዋጋ ፡ እንዴት ፡ በተገኘ ፡ ነበር ።
የዚህ ፡ ዓለም ፡ ዘመኑ ፡ ክፉ ፡ ነውና ፡ ጥቂት ፡ ፴፫፤
ነውና ፡ ይህ ፡ ደገኛ ፡ ዓለም ፡ መንግሥተ ፡ ሰማይ ፡
አለመሰጠቱ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ ነው ፡ ብዬ ፡
መለስሁለት ።
ከእግዚአብሔር ፡ ይልቅ ፡ አንተ ፡ እጅግ ፡ የምት ፴፬፤
ቸኩል ፡ አይደለም ፡ አንተስ ፡ ስለ ፡ ራስህ ፡ ትቸ
ኩላለህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ስለ ፡ ብዙዎች ፡
ጻድቃን ፡ ይቸኩላል ።
የመንግሥተ ፡ ሰማይን ፡ ነገር ፡ የጻድቃን ፡ ነፍ ፴፭፤
ሳት ፡ በማደሪያቸው ፡ ሁነው ፡ ጠየቁ ፡ በዚህ ፡
እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ እንኖራለን ፡ የምግባራች
ንስ ፡ ዋጋ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ የሚሰጠን ፡
እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ ነው ።
መልአኩ ፡ ኢይሩማኤል ፡ እንደናንተ ፡ ያሉ ፡ ፴፮፤
ጻድቃን ፡ ቍጥራቸው ፡ በተፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ ነው ፡
ብሎ ፡ መለሰላቸው ።
ይህ ፡ ዓለም ፡ በሚዛን ፡ ተመዝኗልና ፡ ባሕር ፴፯፤
ንም ፡ በላዳን ፡ ሰፍሮታልና ፡ ( ዘመኑን ፡ በ፰ ፡
ሺህ ፡ ወስኖታልና ፡ ) የተሰጠው ፡ ዘመኑም ፡ እስ
ኪፈጸም ፡ ድረስ ፡ ዝም ፡ ይላል ፡ አያልፍም ።
አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ እነሆ ፡ እኛ ፡ ሁላችን ፡ ኃጢአ ፴፰፤
ትን ፡ የተመላን ፡ ነንና ።
የወዳጆቹን ፡ የጻድቃን ፡ የምግባራቸው ፡ ዋጋ ፡ ፴፱፤
መንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ የሚከለከል ፡ ስለ ፡ ኃጢ

፵፪ ለዘለዓለሙም ፡ ትከብሩበታላችሁና ፡ ቃሌን ፡
አድምጡኝ ፡ አለኝ ።
፵፫ አባቶቻችንም ፡ ሕግህን ፡ ተቀብለው ፡ አልጠበ
ቁም ፡ በሥራትህም ፡ አልፀኑም ፡ ያንተ ፡ ገን
ዘብ ፡ ስለሆነ ፡ ይጠፋ ፡ ዘንድ ፡ አይቻልምና ፡
ከሕግህ ፡ ወገን ፡ ግን ፡ አልጠፋም ።
፵፬ ሕግ ፡ ያንተ ፡ ገንዘብ ፡ ስለሆነች ፡ የሠራላቸውን ፡
ሕግ ፡ አልጠበቁምና ፡ ሕግህን ፡ ተቀብለው ፡ ያል
ጠበቁ ፡ ሰዎች ፡ ጠፉ ።
፵፭ ምድርም ፡ ዘርተውበት ፡ በታበቅል ፡ ባሕርም ፡
መርከቡን ፡ ከጫኑበት ፡ በኋላ ፡ ብታሰጥም ።
፵፮ ያን ፡ ጊዜ ፡ የዚያ ፡ የዘሩ ፡ ጊዜው ፡ ቢሆን ፡ የዚ
ያም ፡ የመርከቡ ፡ ጊዜው ፡ ቢሆን ፡ የዚያም ፡ የመ
ብሉ ፡ የመጠጡ ፡ ጊዜው ፡ ቢሆን ፡ ምድርን ፡
ዳግመኛ ፡ እንዳይዘሩባት ፡ ባሕርንም ፡ ዳግመኛ ፡
መርከብን ፡ እንዳይጭኑበት ፡ በሰቃውም ፡ ዳግ
መኛ ፡ መብል ፡ መጠጥ ፤ እንዳይዘጋጅበት ፡
ሕግን ፡ ተቀብለው ፡ ያፈረሱ ፡ ሰዎች ፡ እንደ
ዚሁ ፡ ይጠፋሉ ።
፵፯ አቅንቼ ፡ በየሁ ፡ ጊዜ ፡ በቀኝ ፡ በኩል ፡ የምታለ
ቅስ ፡ ሴትን ፡ አየሁ ፡ ቃሏን ፡ አሰምታ ፡ ትጮ
ሃለች ፡ ሰውነቷም ፡ ፈጽማ ፡ ታዝናለች ፡ ልብሷ
ንም ፡ ቀዳለች ፡ በራሷም ፡ አመድ ፡ ነስንሳለች ።
፵፰ ያ ፡ ቀድሞ ፡ የማስበው ፡ አሳቤም ፡ ተለየኝ ፡
ወደሷ ፡ ተመልሼ ፡ ምን ፡ ያስለቅስሻል ፡ ልቡና
ሽን ፡ ለምን ፡ ታሳዝኛለሽ ፡ አልኋት ።
፵፱ ጌታዬ ፡ በራሴ ፡ በመጣብኝ ፡ መከራ ፡ አለቅስ ፡
ዘንድ ፡ ተወኝ ፡ ፈጽሜ ፡ እኔ ፡ አዝኛለሁና ፡
ልቡናየም ፡ አዝናለችና ፡ በመከራዬ ፡ ላይ ፡
መከራ ፡ እጨምራለሁ ፡ አለችኝ ።
፶ ምን ፡ ሆንሽ ፡ ንገሪን ፡ አልኋት ።
፶፩ እኔ ፡ ባሪያህ ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ መካን ፡ ነኝ ፡
ሠላሳ ፡ ዘመን ፡ ከባሌ ፡ ጋራ ፡ ስኖር ፡ ልጅ ፡ አል
ወለድሁም ።
፶፪ እኔ ፡ ግን ፡ በዚህ ፡ በሠላሳው ፡ ዘመን ፡ በየጊ
ዜው ፡ በየሰዓቱ ፡ በመዓልትም ፡ በሌሊትም ፡
ወደ ፡ ልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡ እጸልይ ፡ ነበር ።
፶፫ ከዚህ ፡ ከሠላሳ ፡ ዘመን ፡ በኋላ ፡ የባሪያውን ፡
ልመና ፡ እግዚአብሔር ፡ ሰማ ፡ ኀዘኔንም ፡ ሰማኝ ፡
መከራዬንና ፡ ድካሜንም ፡ አይቶ ፡ አንድ ፡ ልጅ ፡
ሰጠኝ ፡ በሱም ፡ እኔን ፡ ፈጽሞ ፡ ደስ ፡ አለኝ ፡
ባሌንም ፡ ደስ ፡ አለው ፡ ያገሬንም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡
ደስ ፡ አላቸው ፡ እግዚአብሔርንም ፡ አመሰግ
ነው ።
፶፬ በብዙ ፡ ድካምም ፡ አሳደግሁት ።
፶፭ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አካለ ፡ መጠን ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡
ሚስት ፡ አጋባሁት ፡ ሠርግን ፡ ሠረግሁለት ።

ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ጫጉላው ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡
ወድቆ ፡ሞተ ።
፪ ከዚህ ፡ በኋላም ፡ ፋናችንን ፡ መብራታችንን ፡
አጥፍተን ፡ እናለቅስ ፡ ዘንድ ፡ ተቀመጥን ፡ ያገ
ሮቼ ፡ ሰዎችም ፡ ሁሉ ፡ ተነሥተው ፡ ይመክሩኝ ፡
ያረጋጉኝ ፡ ጀመሩ ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በማግሥቱ ፡
ቀን ፡ እስከስከተለችው ፡ ሌሊት ፡ ድረስ ፡ ዝም ፡
አልኩ ።
፫ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ሁሉም ፡ ዝም ፡ ባሉ ፡ ጊዜ ፡ እኔን ፡
ማረጋጋት ፡ እኔን ፡ መምከር ። በተወ ፡ ጊዜ ፡
እኔ ፡ ሌሊት ፡ ተነሥቼ ፡ ሸሸሁ ፡ ወደዚህም ፡
ምድረ ፡ በዳ ፡ መጣሁ ።
፬ ለዘላለሙ ፡ በዚህ ፡ እኖራለሁ ፡ እንጂ ፡ እንግ
ዲህ ፡ ወዲህ ፡ ወደ ፡ አገሬ ፡ እንዳልመለስ ፡ ቈረ
ጥሁ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ እጾማለሁ ፡ እስከሞት ፡ ድረስ ፡
አለቅሳለሁ ፡ እንጂ ፡ እህል ፡ አልበላም ፡ ወሀም ፡
አልጠጣም ፡ አልሁ ።
፭ ያ ፡ የማስበው ፡ አሳብም ፡ ተወኝ ፡ መለስኩላት ፡
እንዲህ ፡ አልኋት ፡ ከሴቶች ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡
አንቺ ።
፮ አላዋቂ ፡ ነሽ ፡ ስለ ፡ ጽዮን ፡ ያገኘችንን ፡ የኛን ፡
ልቅሶ ።
፯ አታይምን ፡ ሁላችን ፡ በኀዘን ፡ እንዳለን ፡ መከ
ራንም ፡ ፈጽመን ፡ እንደተቀበልን ፡ አታይምን ።
፰ እኛ ፡ ሁላችንም ፡ ያዘን ፡ ያለቀስን ፡ ነንና ፡ አሁ
ንም ፡ በውነት ፡ ታዝኝ ፡ ታለቅሽ ፡ ዘንድ ፡ ይገ
ባሻል ፡ እኛ ፡ ስለ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ እናዝናለን ፡
አንቺ ፡ ግን ፡ ስለ ፡ አንድ ፡ ልጅሽ ፡ ታዝኛለሽ ፡
ታለቅሻለሽ ።
፱ ምድርን ፡ ጠይቂያት ፡ ትነግርሻለች ፡ ሁላቸው ፡
ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ በሷ ፡ የተፈጠሩ ፡ ብዙ ፡ ልጆ
ቿን ፡ እነሆ ፡ አሕዛብ ፡ መጥተው ።
፲ ፈጽሞ ፡ ለማጥፋት ፡ ማርከው ፡ ወስደዋቸዋልና ፡
ይልቁንም ፡ ይህን ፡ ያህል ፡ ያጠፋባት ፡ ምድር ፡
ልታለቅስ ፡ ይገባታል ።
፲፩ እንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ፈጽሞ ፡ ያለቅስ ፡ ዘንድ ፡
የሚገባው ፡ ማነው ፡ ይህን ፡ ያህል ፡ ብዙ ፡ የጠ
ፋባት ፡ ያለቅስ ፡ ዘንድ ፡ ይገባልን ፡ ወይስ ፡ አንቺ ፡
ስለ ፡ አንድ ፡ ልጅሽ ፡ ታለቅሽ ፡ ዘንድ ፡ ይገባል ።
፲፪ ወይስ ፡ የኔ ፡ ልቅሶ ፡ እንደ ፡ ምድር ፡ ልቅሶ ፡ አይ
ደለም ፡ ትያለሽን ፡ በፃዕር ፡ በገዓር ፡ አምጬ ፡
የወለድኩት ፡ ልጄን ፡ አጥቻለሁና ።
፲፫ ምድር ፡ ግን ፡ ብዙ ፡ አሕዛብ ፡ ወደሷ ፡ እንደ
መጡ ፡ ልጆቿ ፡ እንደዚሁ ፡ ተማርከው ፡ ሂደዋ
ልና ፡ የኔ ፡ ልቅሶ ፡ እንደ ፡ ምድር ፡ ልቅሶ ፡ አይ
ደለም ፡ ትያለሽን ።
፲፬ ነገር ፡ ግን ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ እልሻለሁ ፡ አንቺ ፡
አምጠሽ ፡ ወልደሽ ፡ እንዳሳደግሽው ፡ ምድርም ፡
እንደዚሁ ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ በሷ ፡ ለተፈጠሩ ፡
ሰዎች ፡ ፈጣሪዋ ፡ የሰጣት ፡ ፍሬዋን ፡ ሰጠቻ
ቸው ።
፲፭ አሁንም ፡ ይህንን ፡ ኀዘንሽን ፡ ካንቺ ፡ አርቂ ፡
ያገኘችሽንም ፡ ቅጣትና ፡ መከራ ፡ የታገሺ ፡
ሁኚ ።
፲፮ እግዚአብሔርን ፡ ብታመሰግኝው ፡ ይረዳሻልና ፡
ልጅሽንም ፡ በጊዜው ፡ ጊዜ ፡ ታገኝዋለሽና ፡ በት
ንሣኤ ፡ ዘጉባኤ ፡ በሴቶችም ፡ ዘንድ ፡ መከራን ፡
የታገሽ ፡ ትባያለሽና ፡ ይህንን ፡ ኀዘንሽን ፡ አርቂ ።
፲፯ አሁንም ፡ ወደሀገርሽ ፡ ግቢ ፡ ወደባልሽም ፡ ሒጂ ፡

አልኋት ።
፲፰ እንዲህ ፡ አላደርግም ፡ በዚህ ፡ እሞታለሁ ፡
እንጂ ፡ ወዳገርም ፡ አልገባም ፡ አለችኝ ።
፲፱ ዳግመኛም ፡ ጠየቅኋት ፡ ተናገርኋት ።
፳ ይህንን ፡ ነገር ፡ አታድርጊ ፡ እሺ ፡ በይኝ ፡ ራስሽ
ንም ፡ እንደ ፡ ጽዮን ፡ መከራ ፡ አድርጊ ፡ የኢየ
ሩሳሌምንም ፡ መከራ ፡ አይተሽ ፡ ተረጋጊ ፡ አል
ኋት ።
፳፩ ቤተ ፡ መቅደሳችን ፡ እንደ ፡ ፈረሰ ፡ አታይምን ።
፳፪ ግናይቱ ፡ እንደ ፡ ጠፋ ፡ ምስጋናችን ፡ እንደ ፡ ቀረ ፡
ዘመራ ፡ ዘውዳችን ፡ እንደወደቀ ፡ ተድላ ፡ ደስታ
ችን ፡ እንደጠፋ ፡ የሕጋችን ፡ ማደሪያ ፡ ታቦተ ፡
ጽዮን ፡ እንደ ፡ ተማረከች ፡ ንዋየ ፡ ቅድሳት ፡ እን
ዳደፈ ፡ ምልክታችን ፡ እንደ ፡ ቀረ ፡ ጌቶቻችን ፡
እንደጐሰቈሉ ፡ ካህናቱ ፡ እንደ ፡ ተቃጠሉ ፡ ሌዋ
ውያን ፡ እንደ ፡ ተማረኩ ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻችን ፡
እንደሞቱ ፡ ሚስቶቻችንን ፡ እንደቀሙን ፡ መም
ሮቻችን ፡ እንደ ፡ ተገደሉ ፡ ጕልማሶቻችን ፡ እን
ደ ተገዙ ፡ ወንዶች ፡ ልጆቻችን ፡ እንደ ፡ ተቀሙ ፡
አርበኞቻችን ፡ እንደ ፡ ደከሙ ፡ አታይምን ።
፳፫ ከዚህ ፡ ሁሉ ፡ የሚበልጥ ፡ ታቦተ ፡ ጽዮን ፡
እንደ ፡ ጠፋች ፡ ቀረች ፡ ክቧም ፡ ንዋየ ፡ ቅድ
ሳቷ ፡ ተማርኮ ፡ ሄደ ፡ በጠላቶቻችን ፡ በባቢሎን ፡
ሰዎች ፡ እጅ ፡ ወደቅን ።
፳፬ አንቺም ፡ ብዙ ፡ ኀዘንሽን ፡ ተይ ፡ ኃያል ፡ የሚ
ሆን ፡ ልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡ ይቅር ፡ ይልሽ ፡
ዘንድ ፡ ከድካምሽም ፡ ፈጽሞ ፡ ያሳርፍሽ ፡ ዘንድ ፡
ይህንን ፡ ብዙ ፡ ኀዘንሽን ፡ አርቂ ፡ አልኋት ።
፳፭ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ይኸን ፡ ስናገራት ፡ ድንገት ፡ ፊቷ ፡
ከፀሐይ ፡ ይልቅ ፡ በራ ፡ መልኳም ፡ እንደ ፡ መብ
ረቅ ፡ መልክ ፡ ሆነ ፡ ወደሷ ፡ መቅረብን ፡ ፈራሁ ፡
ልቡናዬም ፡ ደነገጠብኝ ፡ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ይህ ፡
ምንም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ሳስብ ፡ አስደነገጠችኝ ።
፳፮ አሰምታ ፡ ተናገረች ፡ ከነጋገሯ ፡ የተነሣ ፡ ምድር ፡
እስክትነዋወጥ ፡ ድረስ ፡ ድምጿ ፡ እጅግ ፡ የሚ
ያስፈራ ፡ ሆነ ።
፳፯ በየኋትም ፡ ጊዜ ፡ የከበረች ፡ የታነጸች ፡ አገር ፡
ናት ፡ እንጂ ፡ እነሆ ፡ ሴት ፡ አይደለችም ፡ ታላቅ ፡
የሆነ ፡ የመሠረቶቿን ፡ በታ ፡ አየሁ ፡ ፈርቼም ፡
ቃሌን ፡ አሰምቼ ፡ ጮኹ ።
፳፰ አስቀድሞ ፡ ወደኔ ፡ የመጣህ ፡ መልአኩ ፡ አንተ ፡
ዑርኤል ፡ ወዴት ፡ ነህ ፡ ለምን ፡ እንዲህ ፡ አደረ
ግሽኝ ፡ ወደ ፡ ብዙ ፡ ምርምር ፡ እገባ ፡ ዘንድ ፡
ፍጻሜዬም ፡ ለጕስቍልና ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ ልመ
ናዬም ፡ ለተግዳሮት ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ እንዲህ ፡
ለምን ፡ አደረግሽኝ ፡ አልሁ ።
፳፱ እኔ ፡ እንዲህ ፡ ብዬ ፡ ስናገር ፡ እነሆ ፡ ቀድሞ ፡
ወደኔ ፡ የመጣ ፡ ያ ፡ መልአክ ፡ ወደኔ ፡ መጣ ።
፴ እንደ ፡ ሬሳ ፡ ተኝቼ ፡ አገኘኝ ፡ አእምሮዬም ፡
ከኔ ፡ ጋራ ፡ አልነበረም ፡ ቀኝ ፡ እጄን ፡ ይዞ ፡ አነ
ሣኝ ፡ በእግሮቼም ፡ አቅንቶ ፡ አቆመኝ ።
፴፩ መለሰልኝ ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፡ ምን ፡ ሆንህ ፡ ምን ፡
ያስደነግጥሃል ፡ አእምሮህስ ፡ ከንተ ፡ ጋራ ፡ ስለ ፡
ምን ፡ የለም ፡ አለኝ ።
ጥለሽኛልና ፡ ተለይተሽኛልና ፡ ስለዚህ ፡ ነው ፡ ፴፪
እኔም ፡ እንደ ፡ ነገርሽኝ ፡ ወደዚህ ፡ ምድረ ፡
በዳ ፡ መጣሁ ፡ ወደዚህም ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ በመ
ጣሁ ፡ ጊዜ ፡ እነሆ ፡ ማወቅ ፡ የማይቻለኝን ፡
አየሁ ፡ አልሁት ።
እንግዲህስ ፡ እነግርህ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ባለ ፡ አእ ፴፫
ምሮ ፡ ሰው ፡ ቁም ፡ አለኝ ።
ያላየሁትን ፡ አይቻለሁና ፡ የማላውቀውንም ፡ ፴፬
ሰምቻለሁና ፡ ድንገት ።
እንዳልሞት ፡ እንግዲህ ፡ አትለየኝ ፡ እንጂ ፡ ፴፭
አቤቱ ፡ በል ፡ ተናገር ፡ አልሁት ።
ነገር ፡ ግን ፡ ተለይተሽኝ ፡ ልቡናዬ ፡ ይዘነጋ ፡ ፴፮
ይሆንን ፡ ሰውነቴስ ፡ ትጨነቅ ፡ ይሆንን ።
አሁንም ፡ አቤቱ ፡ በጅ ፡ በለኝ ፡ የዚህን ፡ ነገር ፡ ፴፯
ትርጓሜ ፡ ለኔ ፡ ለባሪያህ ፡ ንገረኝ ፡ አልሁት ።
መለሰልኝ ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፡ ይህ ፡ የተሠወረ ፡ ፴፰
ምሥጢር ፡ ስለሆነ ፡ ለወገኖችህ ፡ ብዙ ፡ ታዝ
ናለህና ፡ ስለ ፡ ጽዮንም ፡ ፈጽመህ ፡ ትቈረቈራ
ለህና ፡ ምግባር ፡ ሃይማኖትህን ፡ በየ ፡ ጊዜ ።
ልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡ ገልጦልሃልና ፡ ስለም ፴፱
ትፈራው ፡ ነገር ፡ አስተምርህ ፡ ዘንድ ፡ ስማኝ ፡
አለኝ ።
ነገሩ ፡ ይህ ፡ ነው ፡ ቀድሞ ፡ ስታለቅስ ፡ ያየሀት ። ፵
ታረጋጋትም ፡ ዘንድ ፡ የጀመርህ ፡ ይች ፡ ሴት ። ፵፩
አሁን ፡ ግን ፡ የታነጸች ፡ ሀገር ፡ ትሆንብሃለች ፡ ፵፪
እንጂ ፡ አንተ ፡ እንዳየሃት ፡ ሴት ፡ ያልሆነች ።
የልጅዋን ፡ መከራ ፡ ነግራሃለችና ፡ ልታረጋጋት ፡ ፵፫
የጀመርከ ።
ይች ፡ ያየሀት ፡ ሴት ፡ ዛሬ ፡ የታነጸች ፡ አገር ፡ ፵፬
ሁና ፡ የምታያት ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ናት ።
ይህ ፡ ሠላሳ ፡ ዘመን ፡ መካን ፡ ሆንኩ ፡ ያለችህም ፡ ፵፭
መሥዋዕት ፡ ሳይሰጡ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ የሚኖሩ ፡
ሰዎች ፡ ሦስት ፡ ሺ ፡ ዘመን ፡ ኑረዋልና ፡ መሥ
ዋዕት ፡ ባይሠዉ ፡ ሦስት ፡ ሺ ፡ ዘመን ፡ ኑረዋ
ዋልና ፡ ይህ ፡ ነው ።
ከሦስት ፡ ሺህ ፡ ዘመን ፡ በኋላ ፡ ሰሎሞን ፡ ቤተ ፡ ፵፮
መቅደስን ፡ ሠራ ፡ ያን ፡ ጊዜም ፡ መሥዋዕትን ፡
ሠዋ ፡ ያች ፡ መካን ፡ ሴት ፡ የወለደችውም ፡
ልጅ ።
ይህም ፡ በብዙ ፡ ድካም ፡ አሳደግሁት ፡ ያለችህ ፡ ፵፯
ኢየሩሳሌም ፡ መሥዋዕት ፡ ሳይሠዋባት ፡ የኖረ
ችው ፡ ዘመን ፡ ነው ።
ይህም ፡ ልጅዋ ፡ ወደ ፡ ጫጕላው ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ ፵፰
ወድቆ ፡ ሞተ ፡ ይችም ፡ መከራዋ ፡ አገኘችኝ ፡ ያለ
ችህ ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ጥፋቷ ፡ ነው ።
እነሆ ፡ ለልጆቿ ፡ ታለቅስላቸው ፡ ዘንድ ፡ እንዳ ፵፱
ለች ፡ ያየሃት ፡ አንተ ፡ ግን ፡ ከመከራዋ ፡ ታረጋ
ጋት ፡ ዘንድ ፡ የጀመርህ ፡ ያች ፡ ሴት ፡ ኢየሩሳ
ሌም ፡ ናት ።
አሁንም ፡ ልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡ በፍጹም ፡ ፶
ሰውነትህ ፡ እንድታዝን ፡ በፍጹም ፡ ልቡናህም ፡
እንድትቈረቈር ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ የተሠወረ ፡ ምሥ
ጢር ፡ ነው ፡ የተድላ ፡ የደስታዋን ፡ ጌጥ ፡ የጌ
ትነትዋንም ፡ መገለጽ ፡ ስለሷ ፡ አሳየህ ።

፶፩፥ እግዚአብሔር ፡ ያሳይህ ፡ ዘንድ ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡
አውቄያለሁና ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ።
፶፪፥ ቤት ፡ ባልተሠራበት ፡ በዚህ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡
ትኖር ፡ ዘንድ ፡ እነግርሃለሁ ።
፶፫፥ ልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡ ምሥጢር ፡ ይገልጽ
በት ፡ ዘንድ ፡ ባለው ፡ በታ ።
፶፬፥ የሰው ፡ ሥራ ፡ ሊኖር ፡ አይቻልምና ፡ ስለዚህ ፡
ነገር ፡ የማምብ ፡ መሠረት ፡ ወደሌለበት ፡ ወደ
ዚህ ፡ ትመጣ ፡ ዘንድ ፡ እነግርሃለሁ ።
፶፭፥ አንተ ፡ ግን ፡ እንግዲህ ፡ አትፍራ ፡ ገብተህ ፡ ተድ
ላዋን ፡ ደስታዋን ፡ የሥራዋንም ፡ ጽናት ፡ እይ ፡
እንጂ ፡ ልብህም ፡ አይደንግጥ ።
፶፮፥ ከብዙ ፡ ሰዎች ፡ ይልቅ ፡ አንተ ፡ ራስህን ፡ አስደ
ንቀሃልና ።
፶፯፥ በልዑልም ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ጥቂቶች ፡ ጻድቃን ፡
ጻድቅ ፡ ተብለሃልና ፡ በጆሮህም ፡ የተቻለህን ፡
ያህል ፡ ስማ ።
፶፰፥ ዛሬ ፡ በዚህ ፡ እደር ።
፶፱፥ ልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ በሚ
ኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ በጊዜው ፡ ጊዜ ፡ የሚያደር
ገውን ፡ ራዕይ ፡ ነገ ፡ በሕልም ፡ ያሳይሃል ፡ አለኝ ።
፷፥ በዚያች ፡ ሌሊት ፡ አደርኩ ፡ እንዳዘዘኝ ፡ በማግ
ሥቱም ፡ አደርኩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩፥ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በሌሊቱ ፡ ማግስት ፡ ንስር ፡ ከባ
ሕር ፡ ሲወጣ ፡ በሕልም ፡ አየሁ ፡ (መንግሥት ፡
ባቢሎን ፡) ክንፎችም ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ናቸው ፡
ራሶቹም ፡ ሦስት ፡ ናቸው ።
፪፥ በክንፉም ፡ በዓለሙ ፡ ሁሉ ፡ ይበራል ፡ (በሥል
ጣኑ ፡ ዓለሙን ፡ ሁሉ ፡ ይገዛል ፡) የሰማይ ፡ ነፋሳ
ትም ፡ ሁሉ ፡ ይነፍሱበታል ፡ (መኳንንት ፡) ደመ
ናትም ፡ በሱ ፡ ይሰበሰባሉ ።
፫፥ ከነዚያም ፡ ክንፎቹ ፡ ራሶች ፡ ይበቅላሉ ፡ (ልጆች ፡
ይወልዳሉ ፡) እነዚያም ፡ ራሶች ፡ ቃናናሽ ፡ ክንፍ ፡
ይሆናሉ ፡ ደካሞች ፡ ይሆናሉ ።
፬፥ ራሶቹም ፡ ዝም ፡ ይላሉ ፡ ከነዚያም ፡ ራሶቹ ፡
የመካከለኛው ፡ ራሱ ፡ ይበልጣል ፡ ነገር ፡ ግን ፡
እሱም ፡ ከነሳቸው ፡ ጋራ ፡ ዝም ፡ ይላል ።
፭፥ ያም ፡ ንሥር ፡ ምድርን ፡ ይገዛት ፡ ዘንድ ፡ በም
ድር ፡ ያሉ ፡ ሰዎችንም ፡ ይገዛቸው ፡ ዘንድ ።
፮፥ ከሰማይ ፡ በታች ፡ ያሉ ፡ ሁሉ ፡ ይገዙለት ፡ ዘንድ ፡
በክንፉ ፡ ይበራል ፡ ያንንም ፡ ንስር ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡
ከተፈጠረው ፡ ፍጥረት ፡ የሚከራከረው ፡ የለም ።
፯፥ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ያ ፡ ንሥር ፡ ተነሥቶ ፡ በጥፍሮቹ ፡
ቆሞ ፡ ቃሉንም ፡ አሰምቶ ፡ ጮኸ ።
፰፥ ክንፎቹንም ፡ ሁላችሁ ፡ ከናንተ ፡ አንዱም ፡ አን
ዱም ፡ በየበታችሁ ፡ ተኙ ፡ እንጂ ፡ ሁላችሁ ፡ አን
ድነት ፡ አትነሡ ፡ በየጊዜው ፡ ትነሣላችሁ ።
፱፥ የኋለኛይቱ ፡ ራሱ ፡ ከሁሉ ፡ ትበልጣለች ፡ አለኝ ፡
(ከፋርስ ፡ በኋላ ፡ የተነሣች ፡ መንግሥት ፡ ጽርዕ ፡
ከሁሉ ፡ ትበልጣለች ) ።
፲፥ በየሁ ፡ ጊዜ ፡ የሚገዙ ፡ ከዘመዶቹ ፡ የሚወለ
ደው ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ከሱ ፡ የሚወለደው ፡ አይ
ደለም ። ፡
የነዚያ ፡ የራሶች ፡ ቍጥርም ፡ ስምንት ፡ ናቸው ፡ ፲፩፥
(የሊህ ፡ የነገሥታት ፡ ቍጥርም ፡ ስምንት ፡
ናቸው ) ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በቀኝ ፡ በኩል ፡ ወጣ ፡ ዓለሙ ፲፪፥
ንም ፡ ሁሉ ፡ ገዛ ፡ አለ ። (ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በባ
ቢሎን ፡ ቀኝ ፡ ያለ ፡ መንግሥት ፡ ሚዶን ፡ ተነሣ ፡
ዓለሙንም ፡ ሁሉ ፡ ገዛ ፡)
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ጥፋቱ ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ በታው ፡ ፲፫፥
የማይታይ ፡ እስኪሆን ፡ ድረስ ፡ እሱም ፡ ጠፋ ፡
አለ ፡ ሁለተኛውም ፡ ወጣ ፡ እሱም ፡ ብዙ ፡
ዘመን ፡ አጽንቶ ፡ ገዛ ፡ አለ ፡ (ባልንጀራው ፡
ፋርስ ፡ ተነሣ ፡ ብዙ ፡ ቀንም ፡ አጽንቶ ፡ ገዛ ፡ )
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ የሚጠፋበት ፡ ቀን ፡ በደረሰ ፡ ፲፬፥
ጊዜ ፡ እሱም ፡ እንደ ፡ ፊተኛው ፡ ጠፋ ።
ቃል ፡ መጣለት ። ፲፭፥
ምድርን ፡ ይኸን ፡ ያህል ፡ ዘመን ፡ አጽንተህ ፡ ፲፮፥
የገዛሃት ፡ አንተ ፡ አሞራ ፡ ሳትጠፋ ፡ ይኸን ፡
የምንግርህን ፡ ስማ ፡ አለ ፡ (ዓቢይ ፡ አንጥያኮስ ፡)
ከንተ ፡ በኋላ ፡ እንዳንተ ፡ የሚጸና ፡ የኩሌታህ ፲፯፥
ንም ፡ እኩሌታ ፡ እንዳንተ ፡ የሚገዛ ፡ የለም ፡
(አፊፋኖስ ፡)
ሦስተኛውም ፡ ወጣ ፡ እሱም ፡ ከሱ ፡ አስቀድሞ ፡ ፲፰፥
እንደ ፡ ነበረው ፡ አጽንቶ ፡ ገዛ ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡
እሱም ፡ ጠፋ ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ዳግመኛ ፡ ክንፎቹ ፡ (ነገሥታቱ ፡) ፲፱፥
ሁሉ ፡ ወጡ ፡ እያንዳንዳቸውም ፡ ገዙ ፡ ዳግ
መኛ ፡ ሁሉም ፡ ጠፉ ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አጽንተው ፡ ይገዙ ፡ ዘንድ ፡ በግራ ፡ ፳፥
በኩል ፡ በየጊዜያቸው ፡ ክንፎቹ ፡ (ነገሥታቱ ፡)
ተነሡ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ፈጥነው ፡ ጠፉ ።
ከሳቸውም ፡ የተነሡ ፡ አሉ ፡ ነገር ፡ እነሱ ፡ አል ፳፩፥
ገዙም ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ እሊህ ፡ አሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ክንፎቹ ፡ ፳፪፥
(ነገሥታቱ ፡) ጠፉ ፡ እሊህም ፡ ሁለቱ ፡ ራሶቹ ፡
(ነገሥታቱ ፡) ጠፉ ።
ዝም ፡ ከሚሉ ፡ ከሦስቱ ፡ ራሶቹ ፡ (ነገሥታቱ ፡) ፳፫፥
በቀር ፡ ከዚህ ፡ አሞራ ፡ ወገን ፡ የቀረ ፡ የለም ፡
ከስድስቱ ፡ (ነገሥታቱ ፡) ራሶቹም ፡ በቀር ፡ የቀረ ፡
የለም ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ከሊህ ፡ ከስድስቱ ፡ ራሶቹ ፡ ሁለቱ ፡ ፳፬፥
ተለይተው ፡ ሄዱ ፡ በቀኝ ፡ በኩል ፡ ባለ ፡ ራሱ ፡
ውስጥ ፡ የተቀመጡ ፡ አራቱ ፡ ግን ፡ በበታቸው ፡
ቀሩ ።
እሊህ ፡ አራቱ ፡ ራሶች ፡ (ነገሥታቱ ፡) ግን ፡ ፳፭፥
ይቆሙ ፡ ዘንድ ፡ አለሱም ፡ ይገዙ ፡ ዘንድ ፡ ተማ
ከሩ ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አንዱ ፡ ተነሥቶ ፡ ቆመ ፡ ነገር ፡ ፳፮፥
ግን ፡ ፈጥኖ ፡ ጠፋ ።
ሁለተኛውም ፡ እንደሱ ፡ ከፊተኛው ፡ ይልቅ ፡ ፳፯፥
እሱ ፡ ፈጥኖ ፡ ጠፋ ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ከሞት ፡ የቀሩት ፡ እሊህ ፡ ሁለቱ ፡ ፳፰፥
ነግሠው ፡ ይገዙ ፡ ዘንድ ፡ እንደሱ ፡ ተማከሩ ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ እሊህም ፡ ሲማከሩ ፡ ዝም ፡ የሚሉ ፡ ፳፱፥

ከሦስቱ ፡ ራሶች ፡ መካከለኛ ፡ የሚሆን ፡ አንዱ ፡
ተነሣ ፡ ከነሳቸው ፡ የሚበልጥ ፡ እሱ ፡ ነው ።
፴፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ እሊህን ፡ ሁለቱን ፡ ራሶች ፡ ከሱ ፡
ጋራ ፡ ወሰዳቸው ።
፴፩፤ ያም ፡ ራስ ፡ አብረውት ፡ ካሉ ፡ ጋራ ፡ ተመለሰ ፡
ይገዙ ፡ ዘንድ ፡ የተማከሩ ፡ እሊህን ፡ ሁለቱን ፡
ራሶች ፡ ዋጣቸው ፡ ድል ፡ ነሣቸው ።
፴፪፤ ያም ፡ ራስ ፡ (አፌፋኖስ ፡ አንጥያኮስ ፡ ) አጽንቶ ፡
ገዛ ፡ በሷም ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎችን ፡ በብዙ ፡ ድካም ፡
መከራ ፡ አጸናባቸው ፡ ከቆሙት ፡ ከሊህ ፡ ክን
ፎች ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ፈጽሞ ፡ ዓለምን ፡ ቀማ ።
፴፫፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ መካከለኛው ፡ ራስ ፡ እንደ ፡ እለ
ዚያ ፡ ጠፋ ፡ (አፌፋኖስ ። )
፴፬፤ ሁለቱ ፡ ራሶች ፡ ቀሩ ፡ (ኢጀም ፡ ሮም ፡ ) እነሱም ፡
እንደነሱ ፡ ምድርን ፡ ገዚት ፡ በውስጧ ፡ ያሉት
ንም ፡ ገዟቸው ።
፴፭፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ይህ ፡ በቀኝ ፡ እኩል ፡ ያለው ፡
ራስ ፡ (በጥሊሞስ ፡ ) በግራ ፡ እኩል ፡ ያለውን ፡
ዋጠው ፡ (አንጥያኮስ ፡ )
፴፮፤ በፊትህ ፡ ተመልከት ፡ የምታየውንም ፡ እወቅ ፡
ያለኝን ፡ ቃል ፡ ሰማሁ ።
፴፯፤ ባየሁም ፡ ጊዜ ፡ እየጮኸ ፡ እነሆ ፡ ከምድረ ፡
በዳ ፡ አንበሳ ፡ ተነሣ ፡ እንደ ፡ ሰውም ፡ ሲናገር ፡
ሰማሁት ፡ ያንም ፡ አሞራ ።
፴፰፤ የምነግርህን ፡ እግዚአብሔርም ፡ ያለህን ፡ አንተ ፡
ስማ ።
፴፱፤ ምድርን ፡ ይገዟት ፡ ዘንድ ፡ ከፈጠርኋቸው የዘ
መንም ፡ ፍጻሜ ፡ ከሚደርስባቸው ፡ ከሊህ ፡
ካራት ፡ እንስሳ ፡ (ነገሥታት ፡ ) የቀረህ ፡ አንተ ፡
አይደለህምን ፡ ያለህን ፡ ስማ ።
፵፤ አራተኛውም ፡ መጥቶ ፡ ያለፉትን ፡ በብዙ ፡
ድካም ፡ በብዙ ፡ ሕማም ፡ ይህ ፡ ዓለም ፡ የቀሙ
ትን ፡ እለዚያን ፡ እንስሳ ፡ ሁሉ ፡ ድል ፡ ያደርጋ
ቸዋል ፡ ያለህ ፡ አንተ ፡ ስማ ፡ ይህን ፡ ያህል ፡
ዘመን ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ በተንኰል ፡ ኖሮ ።
፵፩፤ ይችን ፡ ዓለም ፡ በጽኑ ፡ አገዛዝ ፡ ገዛት ፡ ያለህ ፡
አንተ ፡ ስማ ።
፵፪፤ ጻድቃንን ፡ ቀምተሃቸዋልና ፡ ደጋጎቹ ፡ ሰዎች
ንም ፡ በድለሃቸዋልና ፡ ቅኖቹንም ፡ ጠልተህ ፡
አስተኞቹን ፡ ወደሃቸዋልና ፡ የጻድቃንን ፡ አም
ባቸውን ፡ አፍርሰሃልና ፡ ያልበደሉትን ፡ ሰዎች ፡
ቅጽራቸውን ፡ አፍርሰሃልና ።
፵፫፤ ኃጢአትህም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ደርሳለ
ችና ፡ ትቢትህም ፡ ወደ ፡ ኃያል ፡ እግዚአብሔር ፡
ደርሷልና ።
፵፬፤ እግዚአብሔርም ፡ ወገኖቹ ፡ መቃብያንን ፡ በቸ
ርነቱ ፡ ተመልክቷቸኋልና ፡ መቃብያን ፡ መከራ ፡
የሚቀበሉበት ፡ ዘመን ፡ እነሆ ፡ ተፈጽሟልና ።
፵፭፤ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ አንተ ፡ አፌፋኖስ ፡ አንጥያኮስ ፡
ትጠፋለህ ፡ ኃጢአተኞች ፡ ወገኖችህ ፡ የእግዚ
አብሔርን ፡ ሕግ ፡ የዘነጉ ፡ ጥቃቅን ፡ ነገሥታቶ
ችህም ፡ ክፉዎች ፡ የሆኑ ፡ ሠራዊቶችህም ፡ ይጠ
ፋሉ ።
፵፮፤ ምድርም ፡ ከመከራዋ ፡ ሁሉ ፡ እፎይ ፡ ብላ ፡
ከንቱ ፡ ቃርፍ ፡ ዘንድ ፡ የፈጣሪዋን ፡ ቸርነቱንና ፡
ፍርዱን ፡ ተስፋ ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ በደለኞች ፡
ዘመዶችህም ፡ ይጠፋሉ ።

ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ፈጣሪ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለዚያ ፡ ፩፤
ላሞራ ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ በነገረው ።
የቀረው ፡ ይህ ፡ ራስ ፡ ጠፋ ፡ (አፌፋኖስ ፡ ጠፋ ፡ ) ፪፤
ወደሱ ፡ የመጡ ፡ እነዚያም ፡ ክንፎች ፡ (ነገሥ
ታት ) ተነሡ ፡ እሊህም ፡ ይገዙ ፡ ዘንድ ፡ ተነሡ ፡
በጥፍራቸውም ፡ (ሠራዊት ፡ ) ይቃወኩሉ ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ እነሱም ፡ ጠፉ ፡ ሥጋቸውም ፡ ፫፤
ሁሉ ፡ ተቃጠለ ፡ ምድርም ፡ ፈጽማ ፡ ደነገጠች ፡
እኔም ፡ ከብዙ ፡ ምርምር ፡ የተነሣ ፡ ደነገጥሁ ፡
በጽኑ ፡ ፍርሃትም ፡ ነቃሁ ።
ልቡናዬን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሥራ ፡ ስትመረ ፬፤
ምሪ ፡ አንቺ ፡ ይኸን ፡ ሁሉ ፡ አደረግሽኝ ፡ አል
ኋት ።
ሰውነቴ ፡ ደከመች ፡ ልቡናዬም ፡ እጅግ ፡ ተጨነ ፭፤
ቀች ፡ በብዙ ፡ ፍራት ፡ ተይዤ ፡ ምንምን ፡ ኃይል ፡
የለኝ ፡ በዚችም ፡ ሌሊት ፡ ደነገጥሁ ።
ለዘላለሙ ፡ ያጸናኝ ፡ ዘንድ ፡ አሁንም ፡ ወደ ፡ ፮፤
እግዚአብሔር ፡ እለምናለሁ ።
አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ በፊትህ ፡ ባለሟልነትን ፡ ካገ ፯፤
ኘሁ ፡ ባንተ ፡ ዘንድ ፡ ራሴንም ፡ ከስደንቅሁ ፡
ልመናዬም ፡ በፊትህ ፡ ከደረሰች ።
ከመፍራት ፡ አድነህ ፡ አጽናኝ ፡ አልሁት ፡ ልቡ ፰፤
ናዬ ፡ ፈጽማ ፡ ደስ ፡ ይላት ፡ ዘንድ ፡ የሚያስፈራ ፡
የዚህን ፡ የሕልም ፡ ትርጓሜ ፡ ለኔ ፡ ለባሪያህ ፡
ንገረኝ ፡ አልሁ ።
በኋላ ፡ ዘመን ፡ የሚደረገውን ፡ ስለ ፡ ዓለሙ ፡ ፱፤
ወራት ፡ ኅልፈትም ፡ ያሳየኸኝ ፡ አንተ ፡ ደግ ፡
ሰው ፡ አድርገሃልና ፡ ና ፡ የሕልምህን ፡ ትርጓሜ ፡
ንገረኝ ፡ አልሁ ።
ያየኸው ፡ የዚህ ፡ የሕልምህ ፡ ትርጓሜ ፡ እን ፲፤
ዲህ ፡ ነው ፡ አለኝ ።
ከባሕር ፡ ሲወጣ ፡ ያየኸው ፡ ይህ ፡ አሞራ ፡ ለወ ፲፩፤
ንድምህ ፡ ለዳንኤል ፡ በሕልም ፡ የታየችው ፡
አራተኛዋ ፡ መንግሥት ፡ (እስክንድር ፡ ) ናት ።
ዛሬ ፡ ላንተ ፡ እኔ ፡ እንደተረጐምኩልህ ፡ ነገር ፡ ፲፪፤
ግን ፡ ለሱ ፡ አልተረጐምሁለትም ።
እነሆ ፡ ዘመን ፡ ይመጣል ፡ በዚህ ፡ ዓለምም ፡ ፲፫፤
ከሷ ፡ አስቀድሞ ፡ ከነበሩት ፡ መንግሥታት ፡
ይልቅ ፡ የምታስፈራ ፡ መንግሥት ፡ ትነሣለች ።
በሷም ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ነገሥታት ፡ ይነሣሉ ። ፲፬፤
ዳግመኛ ፡ የሚነግሡውም ፡ ካሥራ ፡ ሁለት ፡ ነገ ፲፭፤
ሥታት ፡ በዘመኑ ፡ ፈጽሞ ፡ የሚጸና ፡ ነው ።
ያየሃቸው ፡ የሊህ ፡ ያሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ክንፎች ፡ ፲፮፤
ትርጓሜ ፡ ይህ ፡ ነው ።
ቃልን ፡ ሲናገር ፡ ያየው ፡ ይህም ፡ ከዘመዱ ፡ የተ ፲፯፤
ወለደ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በመንግሥት ፡ ሁለተኛው ፡
የሚሆን ፡ ከሱ ፡ የተወለደ ፡ አይደለም ።
ትርጓሜው ፡ እንዲህ ፡ ነው ፡ ከዚያም ፡ መንግ ፲፰፤
ሥት ፡ አፌፋኖስ ፡ አንጥያኮስ ፡ ይወለዳል ፡ መን

ግሥት ፡ አጠፉ ፡ አጠፉ ፡ ትላለች ፡ በግዛቷ ፡
አጅግ ፡ ጸንታ ፡ ትኖራለች ፡ እንጂ ፡ ነገር ፡ ግን ፡
ያን ፡ ጊዜ ፡ አትጠፋም ።
፲፱ ከክንፎቹ ፡ ራሶች ፡ ሲወጡ ፡ ያየኸውም ፡ ይህ ።
፳ ትርጓሜው ፡ እንደዚህ ፡ ነው ፡ ዘመናቸው ፡
የከፋ ፡ ወራታቸው ፡ ያጠረ ፡ ፰ ፡ ነገሥታት ፡
በሷ ፡ ይነግሣሉ ፡ ሁለቱ ፡ ግን ፡ ከነሳቸው ፡ በዘ
መናቸው ፡ መካከል ፡ ፈጥነው ፡ ይጠፋሉ ።
፳፩ ነገር ፡ ግን ፡ ዓራቱ ፡ መንግሥታት ፡ የሚጠፉ
በት ፡ ጊዜ ፡ እስኪደርስ ፡ ድረስ ፡ ይጠበቃል ፡
ሁለቱ ፡ ነገሥታትም ፡ (አጀም ፡ ሮም ፡) ለብዙ ፡
ዘመን ፡ ይጠበቃሉ ።
፳፪ ገዝም ፡ ብለው ፡ ያየሀቸው ፡ እነዚህም ፡ ሦስቱ ፡
ራሶች ።
፳፫ ትርጓሜው ፡ እንዲህ ፡ ነው ፡ እግዚአብሔር ፡
በኋላ ፡ ዘመን ፡ ሦስቱን ፡ ነገሥታት ፡ ያስነሣል ፡
በውስጧም ፡ እንግዳ ፡ ነገር ፡ ይሠራሉ ፡ ምድር
ንም ፡ መከራ ፡ ነገር ፡ ያጸኑባታል ።
፳፬ ከሳቸው ፡ አስቀድሞ ፡ ከነበሩት ፡ ከነገሥታቱ ፡
ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ በውስጧ ፡ የሚኖሩትንም ፡
ሰዎች ፡ በብዙ ፡ ፍሬት ፡ መከራ ፡ ያጸኑባቸዋል ።
፳፭ የመንግሥት ፡ መገኛ ፡ ናቸውና ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡
ከነገሥታት ፡ በላይ ፡ ተባሉ ።
፳፮ በመኝታው ፡ የሚሞት ፡ ከለሳቸው ፡ አንዱ ፡
እሱ ፡ ብቻ ፡ ነውና ፡ ታላቅ ፡ ራሱ ፡ ሲጠፋ ፡ ያየ
ኸው ፡ ይህ ፡ አንዱ ፡ አንጥያኮስ ፡ ነው ፡ ነገር ፡
ግን ፡ ተጨንቆ ፡ ይሞታል ።
፳፯ የቀሩት ፡ እሊህ ፡ ሁለቱ ፡ ግን ፡ በጦር ፡ ይሞታሉ ።
፳፰ አንዱ ፡ በጥሊሞስ ፡ ኋላ ፡ በጦር ፡ ይሞታል ።
፳፱ በየማናዊ ፡ ሥልጣን ፡ ወደጸና ፡ ወደ ፡ በጥሊ
ሞስ ፡ ሲሔዱ ፡ ያየሀቸው ፡ እሊህ ፡ ሁለቱ ፡
(አጀም ፡ ሮም ፡) ናቸው ።
፴ ትርጓሜው ፡ ይህ ፡ ነው ፡ እግዚአብሔር ፡ ለኋላ ፡
ዘመን ፡ የጠበቃቸው ፡ የጥፋት ፡ መጀመሪያ ፡
የሚደረግባቸው ፡ አጀም ፡ ሮም ፡ ናቸው ፡ አንተ ፡
እንዳየኸውም ፡ ብዙ ፡ ጸብ ፡ ክርክር ፡ ይደረጋል ።
፴፩ ከምድረ ፡ በዳ ፡ እያናፋ ፡ ሲወጣ ፡ ያየኸው ፡ ይህ ፡
አንበሳ ፡ ያን ፡ አሞራ ፡ የተናገረው ፡ በኃጢአ
ቱም ፡ የሰደበው ፡ የሰማሀ ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ ነገር ።
፴፪ እግዚአብሔር ፡ ለኋላ ፡ ዘመን ፡ የጠበቀው ፡ ከዳ
ዊትም ፡ ወገን ፡ የሚወለድ ፡ ይህ ፡ አንበሳ ፡
(ከደቂቀ ፡ ከስሙናይን ፡ አንዱም ፡ አንዱ ፡
ነው ፡) መጥቶም ፡ ኃጢአታቸውን ፡ ይነግራቸ
ዋል ፡ ስለበደላቸውም ፡ ይሰድባቸዋል ፡ በፊታ
ቸውም ፡ ፍዳቸውን ፡ ይገልጥባቸዋል ።
፴፫ በደኅንነታቸው ፡ አስቀድሞ ፡ ያቆማቸዋል ፡ ከሰ
ደባቸውም ፡ በኋላ ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ ያጠፋቸዋል ።
፴፬ ከክህደት ፡ የቀሩ ፡ መቃብያንን ፡ ግን ፡ በቸርነቱ ፡
በክበረ ፡ አውራጃየ ፡ (ኢየሩሳሌም ፡) ያድናቸ
ዋል ፡ አስቀድሜ ፡ የነገርኩህ ፡ ዕለተ ፡ ምጽአ
ትም ፡ እስኪደርስ ፡ ድረስ ፡ ደስ ፡ ያሰኛቸዋል ።
፴፭ ያየኸው ፡ ይህ ፡ ሕልምህ ፡ እንደዚህ ፡ ነው ፡
ትርጓሜውም ፡ እንደዚህ ፡ ነው ።

ይህን ፡ ምሥጢር ፡ታውቀው ፡ ዘንድ ፡ እግዚአ ፴፮
ብሔር ፡ ላንተ ፡ ብቻ ፡ እንድታውቀው ፡ አደረ
ገህ ።
ነገር ፡ ግን ፡ ይህን ፡ ያየኸውን ፡ ሁሉ ፡ በብራና ፡ ፴፯
ጻፈው ፡ በተሠወረ ፡ቦታም ፡ አኑረው ።
ይህን ፡ ምሥጢር ፡ በልቡናቸው ፡ ለመጠበቅ ፡ ፴፰
እንዲቻላቸው ፡ አንተ ፡ ለምታውቃቸው ፡ ላቀ
ቆች ፡ ሰዎች ፡ አስተምራቸው ።
አንተ ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ሊገልጽልህ ፡ የወ ፴፱
ደደውን ፡ታይ ፡ ዘንድ ፡ ዳግመኛ ፡ሰባት ፡ ቀን ፡
በዚህ ፡ ተቀመጥ ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ተለይቶ ፡ ሄደ ፡ እሊህ ፡ ሰባት ፡ ፵
ቀኖች ፡ እንዳለፉ ፡ እኔም ፡ ወዳገር ፡ እንዳልገ
ባሁ ፡ ሰዎቹ ፡ ሁሉ ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ትንሹም ፡
ትልቁም ፡ ወገኖቼ ፡ ሁሉ ፡ ተሰብስበው ፡ ወደኔ ፡
መጡ ።
አንተን ፡ ምን ፡ በደልንህ ፡ እኛን ፡ ትተኸን ፡ ፵፩
በዚህ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ትኖር ፡ ዘንድ ፡ ምንስ ፡
አሳዘንህ ።
ከሚለቀሙት ፡ ፍሬ ፡ ሁሉ ፡ አንድ ፡ ፍሬ ፡ እን ፵፪
ዲቀር ፡ በጨለማ ፡ቦታ ፡ ውስጥም ፡ ፋና ፡ እን
ዲያበራ ፡ በጥልቅ ፡ ባሕርም ፡ ውስጥ ፡ወደብ ፡
መርከቡን ፡ጸጥ ፡ እንዲያደርግ ፡ ከነቢያት ፡ ሁሉ ፡
አንድ ፡ አንተ ፡ ብቻ ፡ ቀርተኸናልና ፡ አንተን ፡
ምን ፡ በደልንህ ፡ አሉኝ ።
ወይስ ፡ ያገኘችን ፡ መከራ ፡ አልበቃችንምን ። ፵፫
በዚያ ፡ የሞቱትን ፡ ሰዎች ፡ እኛ ፡ የምናሻላቸው ፡ ፵፬
አይደለንምና ፡ አንተስ ፡ የምትለየን ፡ ከሆነ ፡
ጽዮን ፡ በተቃጠለች ፡ ጊዜ ፡ በተሻለን ፡ ነበር ፡
አሉት ።
ይኸንን ፡ ተናግረው ፡ ቃላቸውን ፡ አሰምተው ፡ ፵፭
አለቀሱ ።
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ስም ፡ አጠራራችን ፡ ፵፮
አለና ፡ የማይዘነጋን ፡ እሱም ፡ ጽኑ ፡ ነውና ፡
የያዕቆብ ፡ ልጆች ፡ እመኑ ።
የእስራኤልም ፡ ወገኖች ፡ አትዘኑ ፡ ብዬ ፡ መለ ፵፯
ስሁላቸው ።
እኔስ ፡ አልተዋችሁም ፡ ከናንተም ፡ አልርቅም ፡ ፵፰
ነገር ፡ ግን ፡ ወደዚህ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ የመጣሁ ፡
ስለ ፡ ጽዮን ፡ ጥፋት ፡ እለምን ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡
ተድላ ፡ ደስታችንን ፡ ተክትሎ ፡ ስለ ፡ መጣብ
ንም ፡ መከራ ፡ ይቅርታን ፡ እለምን ፡ ዘንድ ፡
ነው ፡ አለ ።
አሁንም ፡ ሁላችሁም ፡ ወደ ፡ ቤታችሁ ፡ ግቡ ፡ ፵፱
እኔም ፡ ወደናንተ ፡ እመጣለሁ ።
ከነዚህም ፡ ወራቶች ፡ በኋላ ፡ ባገራችሁ ፡ ወዳለ ፡ ፶
በታችሁ ፡ ግቡ ፡ እንዳልኋቸው ፡ ሕዝቡም ፡ ወደ ፡
ቤታቸው ፡ ገቡ ።
እኔ ፡ ግን ፡ እንዳዘዘኝ ፡ በዚያ ፡ ቦታ ፡ በምድረ ፡ ፶፩
በዳው ፡ ውስጥ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ተቀመጥሁ ፡ ከም
ድረ ፡ በዳ ፡ ፍሬ ፡ ብቻ ፡ ተመገብሁ ፡ በነዚያም ፡
በሰባቱ ፡ ቀኖች ፡ ከምድረ ፡ በዳው ፡ ቅጠል ፡
በላሁ ።

ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩፤ ከዚህም ፡ ከሰባተኛው ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ በሌሊት ፡
ሕልምን ፡ አየሁ ።
፪፤ እነሆ ፡ጽኑ ፡ ነፋስ ፡ ከባሕር ፡ ሲወጣ ፡ አየሁ ፡ የባ
ሕርም ፡ ማዕበል ፡ ሞገዱ ፡ ሁሉ ፡ ታወከ ።
፫፤ ያ ፡ ነፋስ ፡ በሰው ፡ አምሳል ፡ ከባሕር ፡ ሲወጣ ፡
አያለሁ ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ሰማይ ፡ ደመናዎች ፡
ጋራ ፡ ያ ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ወጣ ፡ ፊቱን ፡
መልሶ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ ሁሉ ፡ በጊዜው ፡ ጊዜ ፡
ወደሱ ፡ ይመጣል ።
፬፤ ቃሉ ፡ እየወጣ ፡ ሁሉ ፡ ከቃሉ ፡ የተነሣ ፡ ይቀል
ጣል ፡ ሰም ፡ እደሮ ፡ ማር ፡ ወደ ፡ እሳት ፡ በቀረበ ፡
ጊዜ ፡ እንዲቀልጥ ፡ ቃሉን ፡ የሰሙ ፡ ሰዎች ፡
ሁሉ ፡ ይቀልጣሉ ።
፭፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ስፍር ፡ ቍጥር ፡ የሌላቸው ፡ ብዙ ፡
ሰዎችን ፡ ከባሕር ፡ የወጣ ፡ ይኸን ፡ ሰው ፡ ይጣ
ሉት ፡ ዘንድ ፡ ከራቱ ፡ ማዕዘን ፡ ሲሰበሰቡ ፡
አየሁ ።
፮፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ታላቅ ፡ ተራራ ፡ ሠራ ፡ በላዩም ፡
ላይ ፡ ተቀመጠ ፡ ( መስቀል ። )
፯፤ ከመስቀል ፡ ያደረሰውን ፡ መርምሬ ፡ ላውቅ ፡
ወደድሁ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ማወቅ ፡ ተሳነኝ ።
፰፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ሊይዙት ፡ የተሰበሰቡ ፡ ( አይ
ሁድ ፡ ) ሁሉ ፡ ፈጽመው ፡ ፈሩ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ይይ
ዙት ፡ ዘንድ ፡ ደፋፈሩ ።
፱፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በከበቡት ፡ ጊዜ ፡ ወደሱም ፡
በመጡ ፡ ጊዜ ፡ በነሱ ፡ ሥልጣኑን ፡ አላጸናባቸ
ውም ፡ ጦሩንም ፡ አላነሣባቸውም ፡ የበዳ ፡ ፀብ
ቱንም ፡ ምንምን ፡ አላነሣባቸውም ።
፲፤ ከአፉ ፡ የእሳት ፡ ማዕበልን ፡ ከከንፈሩ ፡ የእሳት ፡
ነበልባልን ፡ ከንደበቱም ፡ የእሳት ፡ ፍምን ፡
እንደ ፡ ጥልቅ ፡ ነፋስ ፡ አወጣ ፡ እንጂ ፡ ሥልጣ
ኑን ፡ አልገለጸባቸውም ፡ ያ ፡ የእሳት ፡ ማዕበል ፡
ያ ፡ የእሳት ፡ ነበልባል ፡ ያ ፡ የእሳት ፡ ፍሙም ፡
ሁሉ ፡ አንድ ፡ ሆነ ፡ በከበቡት ፡ ሊገድሉትም ፡
ዘንድ ፡ በመጡ ፡ በነዚያ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ እንደ ፡
ጥቅል ፡ ነፋስ ፡ ሆኖ ፡ ወረደባቸው ።
፲፩፤ ከአቃጠሏቸው ፡ ጢስ ፡ ከመዳቸው ፡ ትቢያ ፡
በቀር ፡ ከለሳቸው ፡ የሚድን ፡ እስኪታጣ ፡ ድረስ ፡
ሁሉንም ፡ አቃጠላቸው ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ተነ
ሣሁ ።
፲፪፤ ከተነሣሁም ፡ በኋላ ፡ ያንን ፡ ሰው ፡ ከዚህ ፡ ሲወ
ርድ ፡ አየሁት ፡ ( ክርስቶስን ፡ ) ስምሞች ፡ የሚ
ሆኑ ፡ ብዙ ፡ ሌሎች ፡ ሰዎችን ፡ ወደሱ ፡ ጠራ ።
፲፫፤ ብዙ ፡ ሰዎችም ፡ ወደሱ ፡ መጡ ፡ ( ሐዋርያት ፡ )
ከነሳቸውም ፡ ደስ ፡ ያላቸው ፡ አሉ ፡ ከለሳቸው ፡
ያዘኑም ፡ አሉ ፡ ከለሳቸው ፡ የታሰሩ ፡ አሉ ፡ ከዚህ ፡
በኋላ ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ ደንግጬ ፡
ተነሣሁ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ለመንኩ ።
፲፬፤ ቀድሞ ፡ አንተ ፡ ይህን ፡ ጌትነትህን ፡ ለኔ ፡ ለባር
ያህ ፡ አሳየኸኝ ፡ ልመናዬን ፡ እንድትሰማልኝ ፡
አደረግህልኝ ።
፲፭፤ አሁንም ፡ የዚህ ፡ የሕልሜን ፡ ትርጓሜ ፡ዳግ
መኛ ፡ ንገረኝ ።
ነገር ፡ ግን ፡ እኔስ ፡ እንደምጠራጠረው ፡ በነዚያ ፡ ፲፮፤
ወራቶች ፡ ለነበሩ ፡ ሰዎች ፡ ወዮላቸው ፡ ይልቁ
ንም ፡ ላልነበሩ ፡ ሰዎች ፡ ወዮላቸው ።
በኋላ ፡ ዘመን ፡ የሚቆያቸውን ፡ ገና ፡ ያልደረሰ ፲፯፤
ላቸውን ፡ መንግሥተ ፡ ሰማይን ፡ ባለማወቅ ፡
ክደው ፡ ያዝናሉ ፡ ወዮላቸው ።
በሐሳዊ ፡ መሢሕ ፡ ያሉ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ መከራ ፲፰፤
ውን ፡ ፈጽመው ፡ አውቀውታልና ፡ በዘመኑ ፡
ለነበሩ ፡ ሰዎች ፡ ሁላቸው ።
በዚህ ፡ ሕልም ፡ እንዳየሁ ፡ ጽኑ ፡ ጭንቅ ፡ ብዙ ፡ ፲፱፤
ድካምን ፡ ያያሉና ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ወዮላቸው ፡
ነገር ፡ ግን ፡ ይህ ፡ መከራው ፡ ሳይደርስ ፡ መሞት ፡ ፳፤
ይሻላል ፡ ደመና ፡ ታይቶ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ እን
ዲጠፋ ፡ ቢሞቱ ፡ ይሻላቸዋል ፡ በኋላ ፡ ዘመን ፡
የምታገኛቸውን ፡ መከራ ፡ አያውቁም ።
መለሰልኝ ፡ እንዲህን ፡ የሕልምህን ፡ ትርጓሜ ፡ ፳፩፤
እነግርሃለሁ ፡ ይህን ፡ የምትጠይቀኝንም ፡ ነገር ፡
እተረጒምልሃለሁ ።
ስለሚቀሩት ፡ ሰዎች ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ስለሚኖ ፳፪፤
ሩበትም ፡ ሰዎች ፡ ተናግረሃልና ፡ ትርጓሜው ፡
እንዲህ ፡ ነው ።
በነዚያ ፡ ወራቶች ፡ ያን ፡ መከራ ፡ የሚቀበሉትን ፡ ፳፫፤
ሰዎች ፡ ያም ፡ መከራ ፡ የሚያገኛቸውን ፡ ሰዎች ፡
በእግዚአብሔርም ፡ ዘንድ ፡ ሃይማኖትና ፡ በጎ ፡
ምግባር ፡ ጽናትም ፡ ያላቸውን ፡ ሰዎች ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ይጠብቃቸዋል ።
ነገር ፡ ግን ፡ አስቀድመው ፡ ከሞቱ ፡ ሰዎች ፡ በሐ ፳፬፤
ሳዊ ፡ መሢሕ ፡ ሕያዋን ፡ ሁነው ፡ የተገኙ ፡ ሰዎች ፡
ፈጽመው ፡ ክቡራን ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ ዕወቅ ።
የዚህስ ፡ የሕልምህ ፡ ትርጓሜ ፡ እንደዚህ ፡ ነው ፡ ፳፭፤
ከባሕር ፡ ሲወጣ ፡ ያየኸው ፡ ይህ ፡ ሰው ።
ዓለሙን ፡ ሁሉ ፡ በሱ ፡ ያድን ፡ ዘንድ ፡ ለኋላ ፡ ፳፮፤
ዘመን ፡ አብ ፡ ያዘጋጀው ፡ ይህ ፡ ወልድ ፡ ነው ፡
ከመከራም ፡ የተረፉትን ፡ ሰዎች ፡ እሱ ፡ በተ
ድላ ፡ በደስታ ፡ ያኖራቸዋል ።
እንደ ፡ ጥልቅ ፡ ነፋስ ፡ ሆኖ ፡ ካፉ ፡ እሳት ፡ ነበል ፳፯፤
ባል ፡ የሳት ፡ ፍሕም ፡ ሲወጣ ፡ ያየኸው ።
ጦሩን ፡ ሳያነሣ ፡ የበዳ ፡ ፀብቱን ፡ ሳያነሣ ፡ የከበ ፳፰፤
በትን ፡ እሊህን ፡ ብዙዎችን ፡ ያጠፋቸው ፡ ሊገ
ድሉት ፡ የመጡትንም ፡ ሲያጠፋቸው ፡ ያየኸው ፡
ይህ ፡ ትርጓሜው ፡ እንዲህ ፡ ነው ።
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ያሉትን ፡ ሰዎች ፡ እግዚአብሔር ፡ ፳፱፤
የሚያድንበት ፡ ዘመን ፡ ይመጣል ።
ያን ፡ ጊዜ ፡ እስበሳቸው ፡ ይወነጀላሉ ። ፴፤
በከተማ ፡ ያሉቱ ፡ ሰዎች ፡ በከተማ ፡ካሉት ፡ ፴፩፤
ሰዎች ፡ ጋራ ፡ ይዋጋሉ ፡ በገጠርም ፡ ያሉቱ ፡
ሰዎች ፡ በገጠር ፡ካሉ ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ ይዋጋሉ ፡
ሠራዊት ፡ ከሠራዊት ፡ ነገሥታት ፡ ከነገሥታቱ ፡
ጋራ ፡ ይዋጋሉ ።
ይህም ፡ በተደረገ ፡ ጊዜ ፡ ቀድሞ ፡ ያሳየሁህ ፡ ፴፪፤
ምልክቱም ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ ከባሕር ፡
ሲወጣ ፡ ያየኸው ፡ ያ ፡ ሰው ፡ ይገለጣል ።
ቃሉንም ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ አገ ፴፫፤

ሮቻቸውን ፡ አርስበርሳቸውም ፡ የሚጣሉበትን፡
ጠቦቻቸውንም ፡ ይተዋሉ ።
፵፬፤ ቍጥር ፡ የሌላቸው ፡ ሰዎች ፡ አንድነት ፡ ተሰብ
ስበው ፡ ይበዛሉ ፡ መጥተው ፡ ይገድሉት ፡ ዘንድ ፡
አንድ ፡ ወደዱ ፡ ያየኸው ።
፵፭፤ እሱ ፡ ግን ፡ በመስቀል ፡ ይሰቀላል ።
፵፮፤ መስቀል ፡ ይዘጋጃል ፡ ለሁሉም ፡ ፈጽሞ ፡ ተዘ
ጋጅቶ ፡ ይታያል ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡
ወደ ፡ ተደረገ ፡ በሰው ፡ ፈቃድ ፡ ወዳልተደረገ ፡
ወደ ፡ መስቀል ፡ ሲወጣ ፡ ያየኸው ።
፵፯፤ ኃጢአት ፡ ለመሥራት ፡ እንደ ፡ ዓውሎ ፡ ነፋስ ፡
ፈጣን ፡ የሆኑ ፡ አሕዛብን ፡ በኃጢአታቸው ፡
የሚሰድቡቸው ፡ ተቀዳሚ ፡ ተከታይ ፡ የሌለው ፡
ይህ ፡ ወልድ ፡ ነው ፡ የኃጢአታቸውንም ፡ ፍዳ ፡
በፊታቸው ፡ ይገልጥባቸዋል ፡ ኃጢአትም ፡
ለመሥራት ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ ነበልባል ፡ የሆኑ
ትም ፡ ሰዎች ፡ ጽኑ ፡ ፍዳ ፡ ያመጣባቸዋል ።
፵፰፤ ኃጢአት ፡ ለመሥራት ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ ፍም ፡
የሆኑትን ፡ ሰዎች ፡ ድካም ፡ ሳይኖርበት ፡ ከኃጢ
አታቸው ፡ ጋራ ፡ ያጠፋቸዋል ።
፵፱፤ ስምሞቹ ፡ የሆኑ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ያየሃቸውም ፡
እነዚህ ።
፶፤ እኒህ ፡ በፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ በስልምናሰር ፡ ዘመን ፡
ከገራቸው ፡ የተማረኩ ፡ ስልምናሰር ፡ በነገሠ ፡
ጊዜ ፡ የማረካቸው ፡ በፈሳሹ ፡ ውሃ ፡ ማዶ ፡ ያኖ
ራቸው ፡ ዘጠኙ ፡ ነገድ ፡ ተኩል ፡ ናቸው ፡ ወደ ፡
ሰውቀት ፡ ተመለሱ ፡ ለሰውቀትም ፡ ሌላ ፡ ሆኑ ።
፶፩፤ የወገናቸውን ፡ ነገድ ፡ ይተዉ ፡ ዘንድ ፡ የሰው ፡
ወገን ፡ ወደማይኖርበት ፡ ሀገርም ፡ ይሄዱ ፡
ዘንድ ።
፶፪፤ በሀገራቸው ፡ ሳሉ ፡ ያልጠበቁት ፡ ሕጉን ፡ ይጠ
ብቁ ፡ ዘንድ ፡ እነሣቸው ፡ ይህችን ፡ ምክር ፡ ከል
ቡናቸው ፡ አወጡት ።
፶፫፤ መግቢያቸው ፡ ጠባብ ፡ ወደ ፡ ሆነ ፡ ወደ ፡ ኤፍ
ራጥስም ፡ ገቡ ።
፶፬፤ ያን ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ምልክት ፡ አደረገላ
ቸው ፡ የፈሳሹም ፡ ምንጭ ፡ እስኪያልፉ ፡ ድረስ፡
አቆመላቸው ።
፶፭፤ አገሩ ፡ ግን ፡ ዓመት ፡ ከመንፈቅ ፡ ያስሄዳል ፡ የሀ
ገሩም ፡ ስም ፡ አዛፍ ፡ ይባላል ።
፶፮፤ እስከ ፡ ኋላ ፡ ዘመን ፡ ድረስ ፡ በዚያ ፡ ኖሩ ፡ ከዚ
ህም ፡ ዳግመኛ ፡ ወደየሀገራቸው ፡ ይመለሱ ፡
ዘንድ ፡ ባላ ።
፶፯፤ ይሻገሩ ፡ ዘንድ ፡ የፈሳሹም ፡ ምንጭ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ዳግመኛ ፡ ያቆምላቸዋል ።
፶፰፤ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ሥላሴ ፡ ብዙዎችን ፡ ወሰዷቸው ፡
የአየኸው ፡ ይህ ፡ ነው ፡ እነሱም ፡ በከበረ ፡ መን
ግሥት ፡ ሰማያት ፡ ይገኛሉ ።
፶፱፤ በሱ ፡ የተሰበሰቡ ፡ እነዚያን ፡ ብዙዎች ፡ ሰዎች ፡
ባጠፋቸው ፡ ጊዜ ፤ ያን ፡ ጊዜ ፡ የቀሩትን ፡ ወገ
ኖች ፡ ያጸናቸዋል ።
፷፤ ያን ፡ ጊዜ ፡ ምልክቱን ፡ ያሳያቸዋል ።
፷፩፤ እኔም ፡ አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ ይህንን ፡ ንገረኝ ፡ ከባ
ሕር ፡ መካከል ፡ ሰው ፡ ሲወጣ ፡ እኔ ፡ ያየሁት ፡
ስለ ፡ ምንድነው ፡ አልሁት ።
ማንም ፡ ማን ፡ በጥልቅ ፡ ባሕር ፡ ውስጥ ፡ ያለ ፷፪፤
ውን ፡ ማወቅ ፡ እንዳይችል ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ካሉ ፡
ሰዎችም ፡ ክርስቶስን ፡ እንደዚሁ ፡ ማንም ፡
ማን ፡ ማወቅ ፡ የሚችል ፡ የለም ፡ ሰዓቱ ፡ ቀኑ ፡
በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ከሱም ፡ ጋራ ፡
ያሉት ፡ ሰዎችም ፡ ማወቅ ፡ አይችሉም ።
ያየኸው ፡ የሕልምህም ፡ ትርጓሜው ፡ ይህ ፡ ነው ፡ ፷፫፤
ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ላንተ ፡ ብቻ ፡ አሳየሁህ ።
ግዳጅህን ፡ ትተህ ፡ የኔን ፡ ግዳጅ ፡ ተከትለሃልና ፡ ፷፬፤
ሕጌንም ፡ ፈልገሃልና ።
አነዋወርህን ፡ ለውጠሃል ፡ ተዘጋጅተሃልና ፡ ጥበ ፷፭፤
ብንም ፡ እናት ፡ አድርገሃልና ።
ስለዚህ ፡ ነገር ፡ እንደዚህ ፡ ገለጥሁልህ ፡ ዋጋህ ፡ ፷፮፤
በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ አለና ፡ እንግዲህስ ፡
ወዲህ ፡ ከጥቂት ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ወደኔ ፡ ና ፡ የምነ
ግርህ ፡ ሌላ ፡ ነገር ፡ አለና ፡ ድንቅ ፡ ነገርም ፡ እተ
ረጕምልሃለሁ ፡ ወደኔ ፡ ና ።
እግዚአብሔርን ፡ ፈጽሚ ፡ እያመሰገንሁት ፡ በየ ፷፯፤
ቀኑ ፡ ስለሚያደርገው ፡ ስለ ፡ ታምራቱ ።
ዘመናቱንም ፡ እንደሚሠራው ፡ አድርጌ ፡ በየዘ ፷፰፤
መኑም ፡ እንደሚሠራው ፡ አድርጌ ፡ እግዚአብ
ሔርን ፡ ፈጽሚ ፡ እያመሰገንሁት ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡
በዳ ፡ ሄድኩ ፡ በዚያም ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ አደርሁ ።

ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

በሦስተኛው ፡ ቀን ፡ ከእንጨት ፡ሥር ፡ ተቀ ፩፤
ምጬ ፡ ሳለሁ ።
ከዚያች ፡ እንጨት ፡ አፋዛዣ ፡ ቃል ፡ መጣ ፡ ፪፤
ዕዝራ ፡ ዕዝራ ፡ ብሎ ፡ ጠራኝ ፡ እነሆ ፡ እኔ ፡
አለሁ ፡ አልሁት ፡ ተነሥቼም ፡ ቆምሁ ።
ሙሴን ፡ ፈጽሚ ፡ ታየሁት ፡ ወገኖቼ ፡ እስራ ፫፤
ኤል ፡ ለግብፅ ፡ ሰዎች ፡ በተገዙ ፡ ጊዜ ፡ ጳጦስ ፡
በሚባል ፡ እንጨት ፡ ሥር ፡ ተናገርሁት ።
ወደ ፡ ግብፅ ፡ ላክሁት ፡ ወገኖቼንም ፡ ከግብፅ ፡ ፬፤
አወጣኋቸው ፡ ሙሴንም ፡ ወደ ፡ ደብረ ፡ ሲና ፡
ወሰድሁት ፡ ብዙ ፡ ዘመንም ፡ በኔ ፡ ዘንድ ፡ አኖ
ርሁት ።
ብዙ ፡ ድንቅ ፡ ነገርን ፡ ነገርሁት ፡ የዘመኑንም ፡ ፭፤
ምሥጢር ፡ አሳየሁት ፡ የኋላውንም ፡ ዘመን ፡
ፈጽሚ ፡ ነገርሁት ።
ይህን ፡ ነገር ፡ ተናገር ፡ ይህን ፡ ሠውር ፡ ብዩ ፡ ፮፤
አዘዝሁት ።
አሁንም ፡ ላንተ ፡ የነገርሁህን ፡ ያን ፡ ነገር ፡ ፯፤
ታውቅ ፡ ዘንድ ፡ እነግርሃለሁ ።
ያየኸው ፡ ሕልምህን ፡ የሰማኸውን ፡ ትርጓሜ ፰፤
ውንም ፡ በልቡናህ ፡ ጠብቀው ።
መላእክት ፡ ከሰው ፡ ለይተው ፡ ይወስዱሃልና ፡ ፱፤
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ዓለም ፡ እስኪያልፍ ፡ ድረስ ፡
እንዳንተ ፡ ያሉ ፡ ሰዎች ፡ በሉበት ፡ ቦታ ፡ ከል
ጆች ፡ ጋራ ፡ ትኖራለህና ፡ የሰማኸውን ፡ በልቡ
ናህ ፡ አስተውለው ።
ይህ ፡ ዓለም ፡ የሕፃንነቱ ፡ ወራት ፡ አልፏልና ፡ ፲፤
ዘመኑም ፡ አርጅቷልና ።

፲፩፤ ይህ ፡ ዓለም ፡ የሚያልፍበት ፡ ዘመኑ ፡ ከዓሥር ፡
ተከፍሏልና ፡ እስከ ፡ ዓሥርም ፡ ድረስ ፡ ደርሷ
ልና ።
፲፪፤ የዓሥረኛው ፡ እኩሌታው ፡ ቀርቷልና ።
፲፫፤ አሁን ፡ ቤትህን ፡ አዘጋጅ ፡ ያዘኑትንም ፡ ደስ ፡
አሰኛቸው ፡ አዋቆቻቸውንም ፡ ልብ ፡ አስደርጋ
ቸው ፡ የምታልፍ ፡ ይችንም ፡ ዓለም ፡ ተዋት ።
፲፬፤ የኀዘንን ፡ አሳብ ፡ እንግዲህ ፡ ተው ፡ የፈራሽ ፡
የበሰበሽ ፡ ሰው ፡ አሳብን ፡ ተው ፡ የሚሞት ፡
ሰው ፡ አሳብን ፡ ተው ፡ አለመሞትን ፡ ገንዘብ ፡
አድርግ ፡ እንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡
ፈጥነህ ፡ ትሔድ ፡ ዘንድ ፡ ምግባር ፡ ትሩፋት ፡
ሥራ ።
፲፭፤ ይች ፡ ያየሃት ፡ መከራ ፡ ዛሬ ፡ ደርሳለችና ፡ እን
ግዲህ ፡ ወዲህም ፡ ዳግመኛ ፡ ከሷ ፡ የምትከፋ ፡
መከራ ፡ ትደረጋለች ።
፲፮፤ ዓለም ፡ እያረጀ ፡ እየደከመ ፡ ይሔዳልና ፡ እንደ
ዚህ ፡ ሁሉ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎችም ፡
ክፋታቸው ፡ ትበዛለች ።
፲፯፤ ይህ ፡ ያየኸው ፡ ሐሳዊ ፡ መሢሕ ፡ ይመጣ ፡ ዘንድ ፡
ስለ ፡ ቸኩለ ፡ እውነት ፡ ነገር ፡ ትጠፋለችና ፡ አሰ
ትም ፡ ነገር ፡ ትጸናለች ።
፲፰፤ መለስሁለት ፡ እንዲህ ፡ አልሁት ፡ እንግዲህስ ፡
ወዲህ ፡ በፊትህ ፡ እናገራለሁ ።
፲፱፤ አቤቱ ፡ እኔ ፡ እንዳዘዝከኝ ፡ እሔዳለሁና ፡ በዚህ ፡
ዓለም ፡ ያሉትን ፡ ሰዎች ፡ እኔ ፡ ዛሬ ፡ አስተምራ
ቸዋለሁ ፡ እንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ዳግመኛ ፡ የሚወ
ለዱትን ፡ ሰዎች ፡ ማን ፡ ያስተምራቸዋል ።
፳፤ ይህ ፡ ዓለም ፡ በድንቁርና ፡ አለና ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡
ለሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ዕውቀት ፡ የላቸውም ።
፳፩፤ አሪትህ ፡ ጠፍታለችና ፡ የሠራሃውን ፡ ሥራ ፡
ትሠራው ፡ ዘንድ ፡ ያለህንም ፡ የሚያውቀው ፡
የለም ።
፳፪፤ በፊትህስ ፡ ባለሟልነትን ፡ ካገኘሁ ፡ መንፈስ ፡
ቅዱስን ፡ ላክልኝና ፡ ከጥንቱ ፡ ጀምሮ ፡ በዚህ ፡
ዓለም ፡ የሆነውን ፡ ሁሉ ፡ ልጻፍ ፡ ሊድኑ ፡ የወ
ደዱ ፡ ሰዎች ፡ የደኅንነት ፡ መንገድ ፡ ማግኘት ፡
ሰው ፡ ይችል ፡ ዘንድ ፡ በአሪትህ ፡ እንዳለ ፡ አድ
ርጌ ፡ እጽፍ ፡ ዘንድ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ ላክ
ልኝ ።
፳፫፤ መለሰልኝ ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፡ ሔደህ ፡ ወገኖች
ህን ፡ ሰብስባቸው ፡ እስከ ፡ አርባ ፡ ቀንም ፡ ድረስ ፡
እንዳይፈልጉህ ፡ አትፈልጉኝ ፡ በላቸው ።
፳፬፤ አንተ ፡ ግን ፡ ብዙ ፡ ብራና ፡ ሰብስብ ፡ እነሳቸው ፡
ለጽፈት ፡ ብልሆች ፡ ናቸውና ፡ ሶርያ ፡ ደርብያን ፡
ሰላምያን ፡ ኢቀናን ፡ አሳሄል ፡ እሊህ ፡ አምስ
ቱን ፡ ሰዎች ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ አምጣቸው ።
፳፭፤ ወደዚህ ፡ ና ፡ በልቡናህ ፡ የጥበብ ፡ ዕውቀትን ፡
አሳድርብሃለሁ ፡ ትጽፍ ፡ ዘንድ ፡ ያለህን ፡ ሁሉ ፡
እስክትጨርስ ፡ ድረስ ፡ እንግዲህ ፡ ያቺ ፡ ዕው
ቀት ፡ አትለይህም ።
፳፮፤ በጨረስህም ፡ ጊዜ ፡ ገልጠህ ፡ የምታደርገው ፡
አለ ፡ የምትሠውርም ፡ ነገር ፡ አለ ፡ ለአዋቂዎ
ችም ፡ ታስተምራቸዋለህ ፡ ነገ ፡ በዚህ ፡ ሰዓት ፡
ትጽፍ ፡ ዘንድ ፡ ትጀምራለህ ፡ አለኝ ።
እንደ ፡ አዘዘኝ ፡ ሔጄ ፡ ሕዝቡን ፡ ሁሉ ፡ ሰበሰ ፳፯፤
ብሁ ።
እስራኤል ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ስሙ ። ፳፰፤
አባቶቻችሁ ፡ ቀድሞ ፡ ግብፅ ፡ በሚባል ፡ አገር ፡ ፳፱፤
ኖሩ ፡ ከግብፅም ፡ አወጣቸው ።
የደኅንነት ፡ ሕግን ፡ ተቀብለው ፡ አልጠበቁም ፡ ፴፤
ከነሳቸውም ፡ በኋላ ፡ ያላችሁት ፡ እናንተም ፡
እግዚአብሔርን ፡ ካዳችሁት ።
ምድረ ፡ ርስትን ፡ ሰጠን ፡ ጽዮን ፡ የምትባል ፡ ፴፩፤
ሀገርንም ፡ አወረሰን ፡ እላንተም ፡ አባቶቻች
ሁም ፡ ካዳችሁት ፡ እርሱንም ፡ መበደል ፡ አል
ተዋችሁም ፡ የአዘዛችሁ ፡ የእግዚአብሔር ፡
ሕጉን ፡ አልጠበቃችሁም ።
እውነተኛ ፡ ዳኛ ፡ ነውና ፡ በጊዜው ፡ ጊዜ ፡ የሰ ፴፪፤
ጣችሁን ፡ ቀማችሁ ።
አሁንም ፡ እናንተ ፡ በዚህ ፡ በባቢሎን ፡ አላችሁ ፡ ፴፫፤
ወንድሞቻችሁ ፡ ግን ፡ ከናንተ ፡ ተለይተው ፡
በኢየሩሳሌም ፡ አሉ ።
ልቡናችሁን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ያስገዛችሁት ፡ ፴፬፤
እንደዚሁ ፡ ልቡናችሁን ፡ የገሠፃችሁት ፡ እን
ደሆነ ፡ ሕጉንም ፡ የጠበቃችሁት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
አትሞቱም ።
ከሞት ፡ በኋላ ፡ ቍርጥ ፡ ፍርድ ፡ ያመጣልና ፡ እኛ ፴፭፤
ንም ፡ በሕይወት ፡ እያኖረንምና ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡
የጻድቃን ፡ ስማቸው ፡ ይገለጣል ፡ የኃጢአተ
ኞችም ፡ ሥራቸው ፡ ይገለጣል ።
እናንተ ፡ ወደኔ ፡ የሚመጣ ፡ አይኑር ፡ እስከ ፡ ፴፮፤
አርባ ፡ ቀንም ፡ ድረስ ፡ አትፈልጉኝ ።
እንዳዘዘኝ ፡ እሊህን ፡ አምስቱን ፡ ሰዎች ፡ ይዤ ፡ ፴፯፤
ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳው ፡ ሔደን ፡ በዚያም ፡ ተቀ
መጥን ።
በማግሥቱ ፡ ቃል ፡ ዕዝራ ፡ ዕዝራ ፡ ብሎ ፡ ፴፰፤
ጠርቶ ፡ አፍህን ፡ ክፈት ፡ እኔም ፡ የማጠጣህን ፡
ጠጣ ፡ አለኝ ።
አፌንም ፡ በከፈትሁ ፡ ጊዜ ፡ ውሀ ፡ የተመላ ፡ ፴፱፤
መልኩ ፡ እሳት ፡ የሚመስል ፡ መጠጥን ፡ አጠ
ጣኝ ።
አንሥቼ ፡ ጠጣሁት ፡ ልቡናየም ፡ ፈጽሞ ፡ ዕው ፵፤
ቀትን ፡ ተናገረ ፡ በልቡናየ ፡ ዕውቀት ፡ በዛ ፡ ልቡ
ናየም ፡ ትጠብቀዋለች ፡ ታስበዋለች ።
አፌ ፡ ተከፈተ ፡ እንግዲህ ፡ ወዲህም ፡ ዕውቀት ፡ ፵፩፤
አልተወሰነብኝም ።
ለነዚያ ፡ ላምስቱ ፡ ሰዎች ፡ እግዚአብሔር ፡ ዕው ፵፪፤
ቀትን ፡ ገለጸላቸው ፡ የማያውቁት ፡ ምልክት ፡
የሆነ ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ ቀጥለው ፡ ቀጥለው ፡ ጻፉ ፡
በዚያም ፡ አርባ ፡ ቀን ፡ ተቀመጡ ፡ እነሱስ ፡
ቀን ፡ ቀን ፡ ይጽፉሉ ።
ማታ ፡ ማታ ፡ ይመገቡሉ ፡ እኅል ፡ ይበላሉ ፡ እኔ ፡ ፵፫፤
ግን ፡ ቀን ፡ እጽፋለሁ ፡ ሌሊትም ፡ ዝም ፡ አል
ልም ።
በነዚያ ፡ በአርባው ፡ ቀኖች ፡ ሐያ ፡ አራት ፡ መጻ ፵፬፤
ሕፍት ፡ ተጻፉ ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ እነዚያ ፡ አርባ ፡ ቀኖች ፡ በተፈ ፵፭፤

ጸሙ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተናገረኝ ፡ አስ
ቀድሞ ፡ የጻፍኩትን ፡ ያንን ፡ ገልጠህ ፡ አድር
ገው ፡ ያነበው ፡ ዘንድ ፡ የሚገባው ፡ የማይገበ
ውም ፡ ሁሉ ፡ ያንብበው ።
፶፯ የውቀት ፡ ምሥጢር ፡ የጥበብም ፡ ምሥጢር ፡
እንደ ፡ ፈሳሽ ፡ ውሃም ፡ ያለ ፡ ዕውቀት ፡ ላላ
ቸው ፡ አለቆች ፡ ስሆኑ ።
፶፰ ሰዎች ፡ ታስተምራቸው ፡ ዘንድ ፡ ይህን ፡ ተመ
ልከት ።
፶፱ እንዳዘዘኝም ፡ አደረግሁ ፡ በአራተኛውም ፡
ዘመን ፡ ከሚቈጠሩ ፡ ከብዙ ፡ ሱባዔ ፡ በምስተ
ኛው ፡ ሱባዔ ፡ ይህ ፡ ዓለም ፡ በተፈጠረ ፡ ከምስት ፡
ሺህ ፡ ዘመን ፡ ኋላ ፡ ጨረቃ ፡ ሥርቅ ፡ በደረገች ፡
ጨለማዋን ፡ በአጣች ፡ በአሥረኛው ፡ ቀን ፡ በሦ
ስተኛው ፡ ወር ።
፷ በዘጠና ፡ አንደኛው ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ ጽፎ ፡ ያን ፡
ጊዜ ፡ መላእክት ፡ ዕዝራን ፡ ይዘው ፡ እንደሱ ፡
ያሉ ፡ ደጋግ ፡ ሰዎች ፡ ወዳሉበት ፡ ወደ ፡ ብሔረ ፡
ሕያዋን ፡ ወሰዱት ፡ እሱም ፡ ዕዝራ ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡
ድረስ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ጥበብ ፡ የጻፈ ፡ ተባለ ።

* * *

አነቃቅቶ ፡ ላስጀመረን ፡ አስጀምሮ ፡ ላስፈጸ
መን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በእውነት ፡ ለዘላለሙ ፡
ክብር ፡ ምስጋና ፡ ይግባውና ፡ ዕዝራ ፡ የተናገ
ረው ፡ ነገር ፡ መላ ፡ ተፈጸመ ።
እውነት ፡ ነው ፡ እውነት ፡ ነው ፡ ይሁን ፡ ይሁን ፡
ይደረግልን ።

# መ ጽ ሐ ፈ ፡ ዕ ዝ ራ ፡ ካ ል ዕ ።

ምዕራፍ ፩ ።

፩፤ ኢዮስያስ ፡ ለፈጣሪው ፡ ለእግዚአብሔር ፡
መሥዋዕት ፡ የሚሆን ፡ በጉን ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳ
ሌም ፡ አመጣ ፡ በመጀመሪያ ፡ በሚያዝያ ፡ አሥ
ራራት ፡ ቀን ፡ በጉን ፡ ሠዉ ።
፪፤ ካህናቱን ፡ በየማዕርጋቸው ፡ አቆማቸው ፡ እግዚ
አብሔር ፡ በሚመሰገንበት ፡ በቤተ ፡ መቅደስም ፡
በየሰሞናቸው ፡ ሠራቸው ።
፫፤ ሌዋውያኑንም ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ለተሾሙ ፡
ለካህናቱ ፡ ተገዙ ፡ የንጉሡ ፡ የዳዊት ፡ ልጅ ፡
ሰሎሞን ፡ በሠራው ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ የእግዚ
አብሔር ፡ የሕጉ ፡ ማደሪያ ፡ ታቦተ ፡ ጽዮን ፡ በም
ትመሰገንበት ፡ ሥርዓት ፡ አክብሯቸው ፡ አላ
ቸው ።
፬፤ ታቦተ ፡ ጽዮንን ፡ በጫንቃችሁ ፡ መሸከም ፡ አይ
ገባችሁም ። አሁንም ፡ ፈጣሪያችን ፡ እግዚአብ
ሔርን ፡ አምልኩት ፡ የእስራኤልንም ፡ ወገኖች ፡
ደስ ፡ አሰኟቸው ።
፭፤ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ የዳዊት ፡ ታሪክ ፡ በተጻ
ፈበት ፡ የልጁ ፡ የሰሎሞንም ፡ ገናንነት ፡ በተጻ
ፈበት ፡ መጽሐፍ ፡ በሕዝባችን ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡
በየቦታችሁ ፡ በየሀገራችሁ ፡ በየነገዳችሁ ፡ ተዘ
ጋጁ ፡ የሌዊ ፡ ልጆች ፡ በወንድሞቻችሁ ፡ በእስ
ራኤል ፡ ፊት ፡ እግዚአብሔር ፡ በሚመሰገንበት ፡
በቤተ ፡ መቅደስ ፡ በየቦታችሁ ፡ በየሹመታ
ችሁ ፡ ቁሙ ።
፮፤ በዓልንም ፡ አድርጉ ፡ ለወንድሞቻችሁም ፡ መሥ
ዋዕቱን ፡ አዘጋጁ ፡ ለሙሴ ፡ በተሰጠው ፡ በእግ
ዚአብሔር ፡ ሥርዓት ፡ አድርጉ ፡ አላቸው ።
፯፤ ኢዮስያስም ፡ በዚያ ፡ ላሉ ፡ ሰዎች ፡ ሦስት ፡
እልፍ ፡ ፍየሎችንና ፡ በጎችን ፡ ሦስት ፡ ሺህ ፡
ላሞችን ፡ ሰጣቸው ፡ ለካህናትና ፡ ለወገኖቹ ፡
ለሌዋዊም ፡ ልጆች ፡ ከንጉሥ ፡ ቤት ፡ እንዲህ ፡
ሰጠ ።

በቤተ ፡ መቅደስ ፡ ለተሾሙ ፡ ካህናት ፡ ለዘኬያ ፡ ፰፤
ስና ፡ ለኬልቅያስ ፡ ለሲሉያስም ፡ በዓል ፡ ሊያደ
ርጉበት ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ከስድስት ፡ መቶ ፡ በጎ
ችን ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ በሬችን ፡ እዘ ፡ ሰጠ ።
ሳሚያስና ፡ ኢኮንያስ ፡ ሰብያስና ፡ ወንድሙ ፡ ፱፤
ናትናኤል ፡ ኢዮራምና ፡ ኪያሎስ ፡ ሹማምት ፡
ነበሩ ። ሌዋውያንም ፡ በዓል ፡ ሊያደርጉበት ፡
ሺ ፡ በጎች ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ በሬችን ፡ ሰጣቸው ።
በሥርዓቱም ፡ የጸኑ ፡ ሌዋውያንና ፡ ካህናትም ፡ ፲፤
እንዲህ ፡ መልክም ፡ በዓል ፡ አደረጉ ፡ ቂጣንም ፡
በየነገዳቸው ፡ ተመገቡ ።
በሙሴ ፡ መጣፍ ፡ በኦሪት ፡ እንደ ፡ ተጣፈ ፡ በሕ ፲፩፤
ዝቡ ፡ ፊት ፡ በያባቶቻቸው ፡ ሹመት ፡ መሥዋ
ዕቱን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አቀረቡ ።
በነጋውም ፡ እንደዚሁ ፡ አደረጉ ፡ እንደ ፡ ሥር ፲፪፤
ዓታቸው ፡ በጉን ፡ በእሳት ፡ አጤሱ ፡ መሥዋዕ
ቱንም ፡ በጋን ፡ ቀቀሉ ፡ በብረት ፡ ምጣድም ፡
ጠበሱ ።
ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ በጎ ፡ መዓዛ ፡ ያለውን ፡ መሥ ፲፫፤
ዋዕት ፡ ሰደዱላቸው ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አገልጋ
ዮች ፡ ለሚሆኑ ፡ ለወንድሞቻቸው ፡ ለአሮን ፡
ልጆች ፡ ሠዉላቸው ።
ካህናቱ ፡ ግን ፡ ከብዛቱ ፡ የተነሣ ፡ ከጊዜው ፡ ፲፬፤
እስኪያልፍ ፡ ድረስ ፡ የሰባውን ፡ መሥዋዕት ፡
ሠዉ ፡ ሌዋውያንም ፡ ለራሳቸው ፡ ለወንድሞቻ
ቸው ፡ ለአሮን ፡ ልጆች ፡ ተረፈ ፡ መሥዋዕቱን ፡
አቀረቡ ።
ግናያቱን ፡ የሚያደርሱ ፡ የካህናቱ ፡ የአሳፍ ፡ ፲፭፤
ልጆች ፡ ዳዊት ፡ በሠራው ፡ ሥርዓት ፡ በሹመ
ታቸው ፡ ጠንተው ፡ መሥዋዕቱን ፡ ሠዉ ፡ ከን
ጉሡ ፡ የተሾሙ ፡ ዘካርያስና ፡ አሳፍ ፡ ዐዱን
ስም ፡ ሠዉ ።
የቤተ ፡ መቅደስን ፡ ደጃፍ ፡ የሚዘጉ ፡ በረኞ ፲፮፤
ችም ፡ ሠዉ ፡ ወንድሞቻቸው ፡ ሌዋውያን ፡
ያዘጋጁላቸው ፡ ነበርና ፡ ከሰሞኑ ፡ የሚያጓድል ፡

አልነበረም ።
፲፯፤ የእግዚአብሔርን ፡ መሥዋዕት ፡ አቅርበው ፡
ጨረሱ ።
፲፰፤ ንጉሡ ፡ ኢዮስያስ ፡ እንዳዘዘ ፡ ያንጊዜ ፡ በዓል ፡
አድርገው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡
መሥዋዕታቸውን ፡ አቀረቡ ።
፲፱፤ በነዚያ ፡ ወራቶች ፡ ያሉ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡
ቂጣ ፡ እየበሉ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ የሚያከብሩት ፡
በዓለ ፡ ፋሲካን ፡ አደረጉ ።
፳፤ ከነቢዩ ፡ ከሳሙኤል ፡ ወዲህ ፡ በእስራኤል ፡
ዘንድ ፡ እንደሱ ፡ ያለ ፡ በዓል ፡ አልተደረገም ።
፳፩፤ የእስራኤልም ፡ ነገሥታት ፡ ሁሉ ፡ ኢዮስያስ ፡
እንዳደረገው ፡ ሌዋውያንና ፡ ካህናቱም ፡ ከኢየ
ሩሳሌም ፡ ተማርከው ፡ የነበሩ ፡ ተመልሰው ፡
በዚያ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የሚኖሩ ፡ እስራኤል ፡
ሁሉና ፡ አይሁድም ፡ እንዳደረጉት ፡ በዓል ፡
አላደረጉም ።
፳፪፤ ኢዮስያስ ፡ በነገሠ ፡ በአሥራ ፡ ስምንት ፡ ዘመን ፡
ያንን ፡ በዓል ፡ አደረጉ ።
፳፫፤ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ በተመላበት ፡
ልቡና ፡ ኢዮስያስ ፡ በፈጣሪው ፡ ፊት ፡ የሠራው ፡
ሥራ ፡ ጸንቶ ፡ ኖረ ።
፳፬፤ በቀድሞ ፡ ዘመን ፡ እንደተጻፈ ፡ ከነገሥታቱና ፡
ከሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ወገን ፡ የሚሆኑ ፡ ሰዎች ፡ እግ
ዚአብሔርን ፡ ፈጽመው ፡ ስለበደሉ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ቃሉን ፡ አጸና ፡
ላሳዘኑት ።
፳፭፤ ከዚህም ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ ኢዮስያስ ፡ የሠራው ፡
ሥራ ፡ ይህ ፡ ነው ፡ የግብፅ ፡ ንጉሥ ፡ ፈርዖንም ፡
የኤፍራጥስ ፡ ሰዎችን ፡ ለመውጋት ፡ በአዋጅ ፡
አርበኞችን ፡ ይዞ ፡ በዘመተ ፡ ጊዜ ፡ ኢዮስያስ ፡
ወጥቶ ፡ በጠብ ፡ ተቀበለው ።
፳፮፤ የግብፅ ፡ ንጉሥም ፡ እኔ ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ ምን ፡
ጠብ ፡ አለኝ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ ይሁዳው ፡ ንጉሥ ፡
ላከበት ።
፳፯፤ የኤፍራጥስን ፡ ወንዝ ፡ ሰዎች ፡ እዋጋለሁና ፡
ስለዚህ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ እኔ ፡ ገኸ ፡ ከሚሆን ፡
ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ታዝዤ ፡ የመጣሁ ፡
አንተን ፡ ልወጋ ፡ አይደለም ፡ እግዚአብሔር ፡
ከኔ ፡ ጋራ ፡ በረድኤት ፡ አለ ፡ እሱም ፡ ይረዳ
ኛል ፡ መንገዴን ፡ ልቀቅልኝ ፡ ከእግዚአብሔ
ርም ፡ ጋራ ፡ አትከራከር ፡ አለው ።
፳፰፤ ኢዮስያስም ፡ ከሠረገላዎቹ ፡ ጋራ ፡ ሆኖ ፡ መንገ
ዱን ፡ አለቅም ፡ አለ ፡ አኅዱስ ፡ በሚባል ፡
ምድረ ፡ በዳ ፡ ይዋጋቸው ፡ ዘንድ ፡ ጸና ፡ እንጂ ፡
ሲዋጋ ፡ በነቢዩ ፡ በኤርምያስ ፡ አፍ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ በሱ ፡ የነገረውን ፡ ነገር ፡ መስማት ፡
እምቢ ፡ አለ ።
፳፱፤ አለቆችም ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ኢዮስያስ ፡
ወረዱ ።
፴፤ ኢዮስያስም ፡ ብላቴኖቹን ፡ ተዋግቼ ፡ ደክሚያ
ለሁና ፡ ከሰልፉ ፡ ውስጥ ፡ አውጡኝ ፡ አላቸው ፡
ብላቴኖቹም ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ ከሰልፉ ፡ ውስጥ ፡ አወ
ጡት ።

በሌላ ፡ ሠረገላ ፡ ተቀምጦ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ፴፩፤
ገባ ፡ ከዚያው ፡ ሞቶ ፡ በባቱ ፡ መቃብር ፡ ተቀ
በረ ።
በይሁዳ ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ለኢዮስያስ ፡ አለቀሱ ፴፪፤
ለት ፡ ነቢዩ ፡ ኤርምያስም ፡ ለንጉሡ ፡ ለኢዮስ
ያስ ፡ አለቀሰለት ፡ እስከዚች ፡ ቀን ፡ ድረስም ፡
ወንዶች ፡ ከሴቶች ፡ ጋር ፡ አለቀሱለት ፡ ሥር
ዓት ፡ አድርገው ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ይሠሩት ፡ ዘንድ ፡
ይህ ፡ ለእስራኤል ፡ ወገኖች ፡ ሥርዓት ፡ ሆኖ ፡
ተሰጠ ።
ይህም ፡ ሥርዓት ፡ የይሁዳ ፡ ወግ ፡ ታሪክ ፡ በተጣ ፴፫፤
ፈበት ፡ መጣፍ ፡ ተጣፈ ፡ ኢዮስያስም ፡ የሠራ
ውን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ በለጠግነቱም ፡ የእግዚ
አብሔርንም ፡ ሕግ ፡ ማወቁን ፡ ፊትም ፡ ኋላም ፡
የሠራው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ያሥሩ ፡ ነገድ ፡ የሁ
ለቱ ፡ ነገድ ፡ የእስራኤል ፡ ነገሥታት ፡ ወግ ፡
ታሪክ ፡ በተጻፈበት ፡ መጣፍ ፡ ተጻፈ ።
ሕዝቡም ፡ የኢዮስያስ ፡ ልጅ ፡ ኢዮአክን ፡ ከተ ፴፬፤
ወለደ ፡ ሐያ ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ሆኖት ፡ ሳለ ፡ ስለ ፡
አባቱ ፡ ፈንታ ፡ አምጥተው ፡ አነገሡት ።
ኢኮንያስም ፡ ለእስራኤል ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ፴፭፤
ሦስት ፡ ወር ፡ ነገሠ ፡ የግብፅ ፡ ፈርዖንም ፡ የሚ
ያነግሠው ፡ መስሎ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ገባ ።
ሕዝቡንም ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ መክሊት ፡ ብር ፡ ፴፮፤
አንድ ፡ መክሊት ፡ ወርቅ ፡ አስገበራቸው ።
የግብፅ ፡ ንጉሥ ፡ ፈርዖንም ፡ የይሁዳውንም ፡ ፴፯፤
ንጉሥ ፡ ወንድም ፡ ኢዮአቄምን ፡ በኢየሩሳ
ሌም ፡ አነገሠው ።
ኢዮአቄምም ፡ ሹማምንቱን ፡ አሠራቸው ፡ ወን ፴፰፤
ድሙ ፡ ዘርዮንንም ፡ አሥሮ ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ ሰደ
ደው ።
ለይሁዳ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ በነገሠ ፡ ጊዜ ፡ ኢዮ ፴፱፤
አቄም ፡ ከተወለደ ፡ ሐያ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡
ሆኖት ፡ ነበር ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡
ነገር ፡ አደረገ ።
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደ ፵፤
ነፆር ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ዘመተ ፡ በሰንሰለት ፡
አሥሮ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ሰደደው ።
ናቡከደነፆርም ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚመሰገን ፵፩፤
በት ፡ ንዋየ ፡ ቅድሳቱን ፡ ማርኮ ፡ ወስዶ ፡ በባቢ
ሎን ፡ ባለ ፡ ቤቱ ፡ አኖረው ።
ይህም ፡ የይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ ወግ ፡ ታሪካቸው ፡ ፵፪፤
በተጻፈበት ፡ መጽሐፍ ፡ ተጽፏል ።
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ኤልያቄም ፡ ልጁ ፡ በነገሠ ፡ ፵፫፤
በስምንት ፡ ዘመን ።
ለሦስት ፡ ወር ፡ ከሥር ፡ ቀን ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ፵፬፤
ነገሠ ፡ እርሱም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡
ሥራ ፡ ሠራ ።
በዚያችም ፡ ዓመት ፡ ናቡከደነፆር ፡ እግዚአብ ፵፭፤
ሔር ፡ ከሚመሰገንበት ፡ ንዋየ ፡ ቅድሳት ፡ ጋራ ፡
ወደ ፡ ባቢሎን ፡ አገባው ።
ሴዴቅያስንም ፡ በተወለደ ፡ በ፳፩ ፡ ዘመኑ ፡ በኢ ፵፮፤
የሩሳሌምና ፡ በይሁዳ ፡ አነገሠው ፡ አሥራ ፡
አንድ ፡ ዘመንም ፡ ነገሠ ።

፵፯፤ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ ሠራ ፡
በነቢዩ ፡ በኤርምያስ ፡ አፍ ፡ ከተናገረው ፡ ከእ
ግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ የተነሣ ፡ አልፈራም ።
፵፰፤ ንጉሡ ፡ ናቡከደነፆርም ፡ ሲጼቅያስና ፡ የእግዚ
አብሔርን ፡ ስም ፡ አስጠርቶ ፡ አማለው ፡ ክኅደ ፡
ልቡናውንም ፡ አጸና ፡ ልቡናውንም ፡ አስታበየ ፡
የእስራኤል ፡ ፈጣሪ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሕጉ
ንም ፡ ካደው ።
፵፱፤ ካህናቱና ፡ በሕዝቡ ፡ የተሾሙ ፡ ሹማምንቱ ፡
ከአሕዛብ ፡ በደል ፡ ይልቅ ፡ ፈጽመው ፡ ብዙ ፡
በደልን ፡ በደሉ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ከብሯ ፡
ያለች ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚመሰገንባት ፡ ቤተ ፡
መቅደስንም ፡ በኃጢአት ፡ አሳደፉ ።
፶፤ ይራራላቸዋልና ፡ ለማደሪያው ፡ ለቤተ ፡ መቅ
ደስም ፡ ይራራልና ፡ መክሮ ፡ ይመልሳቸው ፡
ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነቢዩን ፡ ከመልአኩ ፡
ጋራ ፡ ወደ ፡ አባቶቻቸው ፡ ላከ ።
፶፩፤ እነዚያ ፡ ግን ፡ በላከው ፡ መልክተ ፡ ዘበቱበ
ቸው ፡ እግዚአብሔርም ፡ በነቢያት ፡ አድሮ ፡
በተናገረ ፡ ጊዜ ፡ በሕዝቡ ፡ እስኪፈረድባቸው ፡
ድረስ ፡ በነቢያት ፡ ይዘብቱባቸው ፡ ነበር ።
፶፪፤ ጣዖቱን ፡ አንድ ፡ አድርገው ፡ ያመልኩ ፡ ነበርና ፡
የከላውዴዎን ፡ አውራጃ ፡ የምትሆን ፡ የፋርሱ ፡
ነገሥታት ፡ ይዘምቱባቸው ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ።
፶፫፤ ዘምተው ፡ ከቤተ ፡ መቅደስ ፡ አደባባይ ፡ በጦር ፡
ጐልማሶችን ፡ ገደሉ ፡ ለጐልማሳም ፡ ለቆንጆም ፡
ለትልቁም ፡ ለትንሹም ፡ ቢሆን ፡ አልራሩም ፡
ሁሉን ፡ ገደሉ ።
፶፬፤ እግዚአብሔርን ፡ የሚያገለግሉበት ፡ ንዋየ ፡
ቅድሳቱን ፡ ጥቃቅኑንምና ፡ ታላላቁንም ፡ ዕቃ ፡
ሁሉ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ ታቦትንም ፡
ከቤተ ፡ መንግሥት ፡ ዕቃ ፡ ቤትም ፡ ያለውን ፡
ማዋኑን ፡ ሁሉ ፡ ማርከው ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡
ወሰዱ ።
፶፭፤ የእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ ቤተ ፡ መቅደስንም ፡
አቃጠሉ ፡ የኢየሩሳሌምንም ፡ ቅጽሮን ፡ አፈ
ረሱ ፡ ግምቧን ፡ በእሳት ፡ አቃጠሉ ።
፶፮፤ በውጭ ፡ ያለውን ፡ ያማረውንም ፡ ዕቃዋን ፡
ሁሉ ፡ አጠፉ ፡ እግዚአብሔር ፡ በኤርምያስ ፡
አፍ ፡ የተናገረው ፡ ይደርስ ፡ ዘንድ ።
፶፯፤ ከጦር ፡ የቀሩ ፡ ልጆቻቸውንና ፡ ሰዎቻቸውን ፡
የፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ ማርኮ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ወሰ
ዳቸው ።
፶፰፤ ኢየሩሳሌም ፡ ዕረፍት ፡ በምታደርግበት ፡ ያለ ፡
ዩላት ፡ ዘንድ ፡ ሰባ ፡ ዘመን ፡ ይፈጸም ፡ ዘንድ ፡
በጠፉችበት ፡ ወራት ፡ ሁሉ ፡ ከመታረስ ፡ ከመ
ቆፈር ፡ ታርፋለች ።

ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩፤ ከመጀመሪያይቱ ፡ ዘመን ፡ ጀምሮ ፡ የፋርስ ፡
ንጉሥ ፡ ቂሮስ ፡ እስከ ፡ ነገሠበት ፡ ዘመን ፡
ድረስ ፡ እግዚአብሔር ፡ በነቢዩ ፡ በኤርምያስ ፡
አፍ ፡ የተናገረው ፡ ቃል ፡ ተፈጸመ ።
፪፤ እግዚአብሔርም ፡ የፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ የቂሮስን ፡
ልቡና ፡ አነሣሣ ፡ በሚገዛው ፡ አገርም ፡ ሁሉ ፡
አዋጅ ፡ ነገረ ።
የፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ ቂሮስ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡ የእስራ ፫፤
ኤል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔር ፡ እኔን ፡ ለዘለዓለሙ ፡
አነገሠኝ ።
ስለ ፡ እናንተ ፡ የይሁዳ ፡ አውራጃ ፡ በምትሆን ፡ ፬፤
በኢየሩሳሌም ፡ ቤተ ፡ መቅደስን ፡ እሠራለት ፡
ዘንድ ፡ አስነሣኝ ፡ ብሎ ፡ ጻፈ ።
እግዚአብሔር ፡ በረድኤት ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ይኑ ፭፤
ርና ፡ የይሁዳ ፡ ክፍል ፡ ወደምትሆን ፡ ወደ ፡
ኢየሩሳሌም ፡ ወጥቼ ፡ ለእስራኤል ፡ ጌታ ፡ ለእ
ግዚአብሔር ፡ ማደሪያው ፡ ቤተ ፡ መቅደስን ፡
ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ ከወገኖቼ ፡ የመረጠው ፡ ማነው ።
በያገራችሁ ፡ ያላችሁ ፡ ሁሉ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ፮፤
የሚሠሩበት ፡ ወርቁን ፡ ብሩን ፡ በየአውራጃ
ችሁ ፡ ዕርዱ ።
እናንተም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ ቤተ ፡ ፯፤
መቅደስ ፡ የሚሠሩበት ፡ ከብቱንና ፡ ፈረሱን ፡
ስለት ፡ ካለው ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ ፈጸምራችሁ ፡ ሥጡ ፡
አለ ።
በነገደ ፡ ብንያምና ፡ በነገደ ፡ ይሁዳ ፡ አገሮች ፡ ፰፤
የተሾሙ ፡ ሹማምንት ፡ በየነገዳቸው ፡ ያውጡ ፡
ሕዝቡም ፡ ካህናቱም ፡ ሌዋውያንም ፡ ያውጡ ፡
እግዚአብሔር ፡ ልቡናውን ፡ ያነሣሣለት ፡ ሁሉ ፡
በኢየሩሳሌም ፡ ያለ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡
ቤተ ፡ መቅደስን ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ይውጣ ።
በውራጃቸው ፡ ያሉ ፡ ሰዎችም ፡ በወርቅና ፡ ፱፤
በብር ፡ በከብትና ፡ በፈረስ ፡ ስለት ፡ ያለባቸ
ውም ፡ ሰዎች ፡ ቤተ ፡ መቅደስንም ፡ ለመሥ
ራት ፡ ልቡናቸው ፡ የወደደ ፡ ሁሉ ፡ ይርዷ
ቸው ፡ አለ ።
ንጉሡ ፡ ቂሮስም ፡ ናቡከደነፆር ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ፲፤
ማርኮ ፡ ወስዶ ፡ በጣዖቶቹ ፡ ቤት ፡ ያኖረውን ፡
የእግዚአብሔር ፡ ንዋየ ፡ ቅድሳቱን ፡ አወጣ ።
የፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ ቂሮስም ፡ በወጣው ፡ ጊዜ ፡ ፲፩፤
ለጠባቂው ፡ ለሚትረዳጢ ፡ ሰጠው ፡ በይሁዳ ፡
የተሾመ ፡ ሰልምናስም ፡ ከእርሱ ፡ እጅ ፡ ተቀበለ ፡
የወጭቱም ፡ ቁጥር ፡ እንዲህ ፡ ነው ፡ የወርቁ ፡
ወጭት ፡ ሠላሳ ፡ ነው ፡ የብሩም ፡ ወጭት ፡
አንድ ፡ ሺህ ፡ ነው ።
የብሩ ፡ ወጭት ፡ ኻያ ፡ ዘጠኝ ፡ ነው ፡ የወርቁም ፡ ፲፪፤
ጣሳ ፡ ሠላሳ ፡ ነው ።
የብሩም ፡ ጣሳ ፡ ሁለት ፡ ሺህ ፡ ከራት ፡ መቶ ፡ ፲፫፤
አሥር ፡ ነው ።
ተመቶ ፡ የተሠራ ፡ ሌላ ፡ የጥቃቅኑ ፡ ዕቃ ፡ ሺ ፡ ፲፬፤
ነው ።
ስልምናሶር ፡ ከወሰደው ፡ ምርኮ ፡ ጋራ ፡ በባቢ ፲፭፤
ሎን ፡ የተቀበለው ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ያገ
ባው ፡ የብሩም ፡ የወርቁም ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ አንድ ፡
ሆኖ ፡ አምስት ፡ ሺ ፡ ከራት ፡ መቶ ፡ ስሳ ፡ ዘጠኝ ፡
ነው ።
የፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ አርጤክስስ ፡ በኢየሩሳሌምና ፡ ፲፮
በይሁዳ ፡ አውራጃ ፡ ከነዚያ ፡ ወገን ፡ ያስቆጠሩ
ቸውም ፡ እሉ ፡ ሚጥራዳጢና ፡ ቤልሞስ ፡ ራቲ

ሞስና ፡ ጠቢልዮስ ፡ ጸሐፊ ፡ የሚሆን ፡ ሲሳዮስና ፡ ብሔል ፡ ቢጤልሞስ ፡ ከነዚህ ፡ በታች ፡ የተሾሙ ፡ እሊህ ፡ በሰማርያ ፡ የሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡ በሌላም ፡ አገር ፡ ያሉ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ።

፲፯ ከባሮችህ ፡ ጸሐፊ ፡ ከሚ ፆን ፡ ከሰሚልዮስና ፡ ከሚሰግድልህ ፡ ከራቲምስ ፡ በፊንቂና ፡ የሶርያ ፡ ክፍል ፡ በምትሆን ፡ በቂሌ ፡ ያሉና ፡ ከነርሳቸው ፡ በታች ፡ ከተሾሙ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ የተላከች ፡ መልእክት ፡ ለጌታችን ፡ ለንጉሡ ፡ ለአርጤክስስ ፡ ትድረስ ፡ ብለው ፡ ክታብን ፡ ጻፉ ።

፲፰ አሁንም ፡ ጌታችን ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ፡ ይህን ፡ ታውቅ ፡ ዘንድ ፡ መቅደሷንና ፡ ቤተ ፡ መንግሥቱን ፡ ቅጽሯንና ፡ አደባባዩን ፡ አድሰው ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ እነሆ ፡ ከንተ ፡ ወደኛ ፡ የመጡ ፡ አይሁድ ፡ ተንከለኛ ፡ ከዳተኛ ፡ አገር ፡ ወደምትሆን ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ሔዱ ።

፲፱ ያች ፡ አገር ፡ ከተሠራች ፡ ቅጽሯም ፡ ካለቀ ፡ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ግብር ፡ አይገብሩም ፡ ዳግመኛም ፡ መንግሥታችንን ፡ ቀምተው ፡ ቤተ ፡ መቅደስን ፡ አሳምረው ፡ ይሠራሉ ።

፳ አሁንም ፡ ቸል ፡ አትበል ፡ ስለዚህም ፡ ነገር ።

፳፩ ያባቶቻችሁ ፡ ወግ ፡ ታሪክ ፡ ከተጻፈበት ፡ መጽሐፍ ፡ ይፈልጉ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ቂሮስ ፡ ላክ ።

፳፪ ያቺ ፡ ሀገር ፡ በገሩ ፡ ሁሉ ፡ ያሉ ፡ ነገሥታትን ፡ እንድታስከዳ ፡ ስለዚህ ፡ የተጻፈ ፡ ወግ ፡ ታሪክ ፡ ታገኛለህ ።

፳፫ አይሁድም ፡ ከአያቶቻቸው ፡ ጀምሮ ፡ ከዳተኞች ፡ እንደሆኑ ፡ ተጽፎ ፡ ታገኛለህ ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ያች ፡ አገር ፡ ትጥፋ ።

፳፬ አሁንም ፡ ጌታችን ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ፡ ነገር ፡ እንነግርህ ፡ ያች ፡ አገር ፡ ከተሠራች ፡ ቅጽሯም ፡ ከተፈጸመ ፡ በኋላ ፡ ከዚያ ፡ ወደፊንቂና ፡ የሶርያ ፡ ክፍል ፡ ወደምትሆን ፡ ወደቂሌ ፡ አያሳልፏችሁም ፡ አሉት ።

፳፭ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ንጉሡ ፡ ለቤሔልማቴምና ፡ በጻፈለት ፡ ለራቲምስ ፡ ለጻፈው ፡ በሰሚልያስም ፡ በፊንቂስና ፡ በሰማርያ ፡ ለሚኖሩ ፡ ከነሳቸው ፡ በታች ፡ ለሚሆኑ ፡ ለቀሩትም ፡ እንዲህ ፡ የምትል ፡ ደብዳቤ ፡ እንደጻፉለት ፡ ጻፈባቸው ።

፳፮ እኔም ፡ የላካችሁትን ፡ ደብዳቤ ፡ አንብቤ ፡ ይፈልጉ ፡ ዘንድ ፡ አዘዝሁ ፡ ያቺም ፡ ሀገር ፡ ከያቷ ፡ ከቀደመ ፡ አያቷ ፡ ጀምሮ ፡ ነገሥታቱን ፡ የምትከዳ ፡ እንደ ፡ ሆነች ።

፳፯ ሰዎችም ፡ ከዳተኞች ፡ እንደሆኑ ፡ ሥራቸውም ፡ ሰልፍ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የኢየሩሳሌምም ፡ ነገሥታት ፡ አርበኞችም ፡ ክፉዎች ፡ የፊንቂስምና ፡ የሶርያ ፡ ክፍል ፡ የምትሆን ፡ ቂሌንም ፡ እንደተገዙላቸው ፡ አገኙ ።

፳፰ አሁንም ፡ እነዚያ ፡ ሰዎች ፡ ያቺን ፡ አገር ፡ መሥራትን ፡ ይከለክሏቸው ፡ ዘንድ ፡ እነሆ ፡ አዘዝሁ ።

፳፱ ነገሥታት ፡ በሚደክሙ ፡ ገንዘብ ፡ ክፋትን ፡ እንዳታበዛ ፡ በውስጧ ፡ ምንምን ፡ የሚሠራ ፡ ሰው ፡ አይኑር ።

፴ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ጸሐፊ ፡ የሚሆን ፡ ስልምዮስና ፡ ራቲሞስ ፡ ከነዚያም ፡ በታች ፡ የተሾሙ ፡ ሹማምት ፡ ንጉሡ ፡ አርጤክስስ ፡ የጻፋትን ፡ ያቺን ፡ ክታብ ፡ ባነበቧት ፡ ጊዜ ፡ ከብዙ ፡ ሠራዊት ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ በብዙ ፡ ችኮላ ፡ ፈረሶቻቸውን ፡ አስነው ፡ የሚሠሩትን ፡ ይከለክሉ ፡ ጀመሩ ።

፴፩ ኢየሩሳሌም ፡ ቤተ ፡ መቅደስም ፡ ሥራ ፡ የፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ ዳርዮስ ፡ እስከ ፡ ነገሠበት ፡ እስከ ፡ ሁለተኛይቱ ፡ ዘመን ፡ ድረስ ፡ መሠራቱ ፡ ቀረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ ንጉሡ ፡ ዳርዮስም ፡ በሚገዛው ፡ ቤተ ፡ ሰዎችና ፡ በግዛቱ ፡ ላሉ ፡ በፋርስ ፡ በሜዶን ፡ ላሉ ፡ መኳንንት ፡ ሁሉ ።

፪ ዕራቅ ፡ ማሠሮችና ፡ ለደጃዝማቾች ፡ ሁሉ ፡ መቶ ፡ ኻያ ፡ ሰባት ፡ ምስፍና ፡ ላሉባት ፡ ለሕንደኬ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉና ፡ ለሹማምንቱ ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ድረስ ፡ ላሉ ፡ ሰዎች ፡ ደግ ፡ በዓል ፡ አደረገ ።

፫ በልተው ፡ ጠጥተው ፡ ጠገቡ ፡ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ቤታቸው ፡ ገቡ ፡ ንጉሡ ፡ ዳርዮስ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ እልፍኙ ፡ ገብቶ ፡ ተኛ ።

፬ ንጉሡን ፡ የሚጠብቁት ፡ ሦስት ፡ ራስ ፡ ጠባቂዎች ፡ ባለሚሎች ፡ ነበሩ ።

፭ ኑ ፡ ሁላችን ፡ መርጠን ፡ አንድ ፡ አንድ ፡ ቃል ፡ እንናገር ፡ የሚወደድ ፡ ነገር ፡ መርጠን ፡ አሻሽለን ፡ እንናገር ፡ ከባልንጀራው ፡ ነገሩ ፡ በዕውቀት ፡ ለበለጠለት ፡ ሰው ፡ ንጉሡ ፡ ዳርዮስ ፡ ብዙ ፡ ገንዘብ ፡ ይስጠው ፡ ነገሩ ፡ በመወደድ ፡ ድል ፡ ስለ ፡ ነሣ ፡ ዋጋ ፡ ድርጎ ፡ ይዳርገው ።

፮ ነጭ ፡ ሐር ፡ ያልብሰው ፡ በወርቅ ፡ ዋንጫም ፡ ይጠጣ ፡ በወርቅ ፡ አልጋም ፡ ይተኛ ፡ የወርቅ ፡ ሠረገላም ፡ ይቀመጥ ፡ ነጭ ፡ ሐርም ፡ ይልበስ ፡ በአንገቱም ፡ ዝርግፍ ፡ ወርቅ ፡ ይሠር ።

፯ ነገሩ ፡ ስለ ፡ ተወደደለት ፡ ከንጉሥ ፡ ቀጥሎ ፡ ይቀመጥ ፡ የንጉሥ ፡ ባለሟል ፡ ይሁን ።

፰ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ሁሉም ፡ ቃላቸውን ፡ጽፈው ፡ አትመው ፡ ከንጉሡ ፡ ከዳርዮስ ፡ መከዳ ፡ በታች ፡ አኖሩት ።

፱ ከዕንቅልፉም ፡ በተነሣ ፡ ጊዜ ፡ ያቺን ፡ ደብዳቤ ፡ እንሰጣታለን ፡ ነገሩ ፡ ለተወደደለት ፡ ንጉሥ ፡ በፋርስ ፡ ያሉ ፡ ሦስቱ ፡ ባለሟሎቹ ፡ በዚሁ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ ይፍረዱለት ፡ አሉ ።

፲ አንዱ ፡ ወይን ፡ ያሸንፋል ፡ ብሎ ፡ ጻፈ ።

፲፩ ሁለተኛውም ፡ ንጉሥ ፡ ያሸንፋል ፡ ብሎ ፡ ጻፈ ።

፲፪ ሦስተኛውም ፡ ሴቶች ፡ ያሸንፋሉ ፡ ከነዚህ ፡ ሁሉ ፡ እውነት ፡ ነገር ፡ ታሸንፋለች ፡ ብሎ ፡ ጻፈ ።

፲፫ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ንጉሡ ፡ በነቃ ፡ ጊዜ ፡ ያቺን ፡ መጽሐፍ ፡ አንሥተው ፡ ሰጥተው ፡ አነበበት ።

፲፬ በሜዶንና ፡ በፋርስ ፡ ያሉ ፡ ዕራቅ ፡ ማሠሮችን ።

፲፭ ሹማምንቱንና ፡ ደጃዝማቾችን ፡ አለቆችንና ፡ መኳንንቶችን ፡ ይመጡ ፡ ዘንድ ፡ ላከ ፡ ያችንም ፡

መጽሐፍ ፡ ተቀምጠው ፡ በፊታቸው ፡ አነበ
ቢት ።
፲፯ ንጉሡ ፡ አሊያን ፡ ሦስቱን ፡ ሰዎች ፡ ጥሯቸው ፡
ራሳቸው ፡ መጥተው ፡ ነገራቸውን ፡ ይናገሩ ፡
አለ ፡ ጠርተዋቸው ፡ ወዳዳራሹ ፡ ገቡ ።
፲፰ በሉ ፡ ነገራችሁን ፡ ተናገሩ ፡ አላቸው ፡ ወይን ፡
ያሸንፋል ፡ ብሎ ፡ መጀመሪያ ፡ የተናገረው ፡ ይና
ገር ፡ ጀመረ ።
፲፱ እንዲህ ፡ አለ ፡ እናንተ ፡ ሰዎች ፡ ወይን ፡ የሚ
ጠጣውን ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ እንዲያሸንፈው ፡ አእ
ምሮውንም ፡ እንዲያሳጣ ፡ አስተውሉ ፡ ብሎ ፡
ተነናገረ ።
፳ የድኃውንና ፡ የንጉሡን ፡ የጌታውንና ፡ የባሪያ
ውን ፡ የባለጸጋውንና ፡ የድኃውንም ፡ ልቡና ፡
አንድ ፡ ያደርገዋል ።
፳፩ የሰውን ፡ ሁሉ ፡ ልቡና ፡ ወደተድላ ፡ ደስታ ፡
መልሶ ፡ ደስ ፡ ያሰኛቸዋል ፡ ኃዘኑን ፡ ሁሉ ፡ አያ
ስቡትም ፡ ግዳጁንም ፡ ሁሉ ፡ አያስቡትም ።
፳፪ የሰውን ፡ ሁሉ ፡ ልቡና ፡ ደርሶ ፡ ባለጸጋ ፡ ያደ
ርገዋል ፡ ንጉሡንም ፡ አያከብረውም ፡ ፈጣሪያ
ቸውንም ፡ አያስቡትም ፡ ሰውን ፡ ሁሉ ፡ ጽኑ ፡
ጽኑ ፡ ነገር ፡ ያናግረዋል ።
፳፫ በጠጡትም ፡ ጊዜ ፡ ወዳጅ ፡ ወዳጁን ፡ ወንድም ፡
ወንድሙን ፡ ይረሳዋል ፡ አምባጓሮ ፡ አስነሥቶ ፡
ሾተላቸውን ፡ ያማዝዛቸዋል ።
፳፬ ከሥካራቸውም ፡ በነቁ ፡ ጊዜ ፡ ያደረጉትን ፡ አያ
ስቡትም ።
፳፭ እናንተ ፡ ሰዎች ፡ ያለውድ ፡ በግድ ፡ እንዲህ ፡
የሚያደርግ ፡ ወይን ፡ አያሸንፍም ፡ ትላላችሁን ፡
አላቸው ፡ እርሱም ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናግሮ ፡
ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ዝም ፡ አለ ።

ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ ንጉሥ ፡ ያሸንፋል ፡ ብሎ ፡ የተናገረው ፡ ሁለ
ተኛውም ፡ ይናገር ፡ ጀመረ ።
፪ እናንተ ፡ ሰዎች ፡ ምድርን ፡ ሰዎች ፡ የሚያሸን
ፏት ፡ አይደለምን ፡ ባሕርንም ፡ በሚገዚት ፡ በው
ስጧ ፡ ያለውንም ፡ ሁሉ ፡ የሚገዙ ፡ አይደለምን ።
፫ የነዚህ ፡ ሁሉ ፡ ጌታቸው ፡ ነው ፡ ፈጽሞ ፡ ይገ
ዛቸዋል ፡ እርሱ ፡ ያዘዛቸውንም ፡ ሁሉ ፡ ይሠ
ራሉ ።
፬ በልንጀራችሁንም ፡ ግደሉ ፡ ቢላቸው ፡ ይገድ
ላሉ ፡ ወደ ፡ ሰልፍም ፡ ሂዱ ፡ ቢላቸው ፡ ይሄ
ዳሉ ፡ ተራሮችንም ፡ ንዳችሁ ፡ ሚዳ ፡ አድር
ጉት ፡ ቢላቸው ፡ ይንዳሉ ፡ አጥሩን ፡ ግንቡን ፡
አፍርሱ ፡ ቢላቸው ፡ ያፈርሳሉ ።
፭ የንጉሡን ፡ ትእዛዝ ፡ እምቢ ፡ እንዳይሉ ፡ ያላቸ
ውን ፡ ይገድላሉ ፡ እነርሳቸውንም ፡ ይገድሏቸ
ዋል ፡ ንጉሥም ፡ ድል ፡ ቢነሣ ፡ የማረኩትን ፡
ምርኮ ፡ ሁሉ ፡ ለንጉሥ ፡ ይመልሳሉ ።
፮ ያልዘመቱ ፡ ያልተዋጉ ፡ ምድርንም ፡ የሚያርሱ ፡
ሰዎችንም ፡ ዘርተው ፡ አዝመራቸውን ፡ በገቡ ፡
ጊዜ ፡ ግብሩን ፡ ለንጉሥ ፡ ይሰጣሉ ።
፯ እርሱ ፡ ግን ፡ አንድ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ ግረፉ ፡ ቢላ
ቸውም ፡ በግድ ፡ ባልንጀራቸውን ፡ ይምቱ ፡
ቢላቸው ፡ ይመታሉ ፡ ተዉ ፡ ቢላቸው ፡ ይተ
ዋሉ ።
ግረፉ ፡ ቢላቸውም ፡ ይገርፋሉ ፡ ሥሩ ፡ ቢላቸ ፰
ውም ፡ ይሠራሉ ፡ አፍርሱ ፡ ቢላቸው ፡ ያፈር
ሳሉ ።
ቍረጡ ፡ ቢላቸው ፡ ይቆርጣሉ ፡ ትከሉ ፡ ቢላ ፱
ቸው ፡ ይተክላሉ ።
ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ሠራዊቱ ፡ ሁሉ ፡ ላንድ ፡ ንጉሥ ፡ ፲
ይገዙታል ፡ ይህም ፡ ይህ ፡ ነው ፡ ከዚህም ፡
ጋራ ፡ እሱ ፡ ተቀምጦ ፡ በልቶ ፡ ጠጥቶ ፡ ይተ
ኛል ።
ሌላው ፡ ዙሪያውን ፡ ከቦ ፡ ይጠብቃል ፡ ከተኛ ፡ ፲፩
በኋላ ፡ ከነርሱ ፡ አንዱ ፡ ሄዶ ፡ ጉዳዩን ፡ ማድ
ረግ ፡ የሚችል ፡ የለም ፡ ሌት ፡ ከዘብ ፡ አደሩ ፡
ቀን ፡ ከጀብ ፡ ዋሉ ፡ ቢላቸው ፡ እምቢ ፡ ይሉት ፡
ዘንድ ፡ አይችሉም ።
እናንተ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ ሆኖ ፡ የሚታ ፲፪
ዘዝለት ፡ ንጉሥ ፡ አያሸንፍም ፡ ትሉላችሁን ፡
አለ ፡ ይህንን ፡ ተናግሮ ፡ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ዝም ፡
አለ ።
ጽድቅና ፡ ሴት ፡ ያሸንፋሉ ፡ ያለ ፡ ሦስተኛውም ፡ ፲፫
ይናገር ፡ ጀመረ ፡ ይኸውም ፡ ዘሩባቤል ፡ ነው ።
እናንተ ፡ ሰዎች ፡ ንጉሡ ፡ ከሁሉ ፡ የሚበልጥ ፡ ፲፬
አይደለምን ፡ ለንጉሡስ ፡ የሚገዙ ፡ ሰዎች ፡ ብዙ ፡
አይደሉምን ፡ ወይንስ ፡ ብርቱ ፡ አይደለምን ፡
እኒህንስ ፡ የሚገዛቸው ፡ የሚያዛቸው ፡ ማነው ።
ንጉሡን ፡ የወለዱት ፡ ሴቶች ፡ አይደሉምን ፡ ፲፭
ምድርና ፡ ባሕርን ፡ የሚገዙ ፡ ሰዎችንስ ፡ ሁሉ ፡
የወለዱ ፡ ሴቶች ፡ አይደሉምን ።
ከነርሳቸው ፡ ተወለዱ ፡ ወይን ፡ ከርሱ ፡ የሚገኝ ፲፮
በት ፡ የወይን ፡ ሐረግን ፡ የሚተክሉ ፡ ሰዎችን ፡
ወልደው ፡ የሚያሳድጉ ፡ ሴቶች ፡ አይደሉምን ።
ፈትለው ፡ ሰፍተው ፡ ወንዶችን ፡ የሚያከብሩ ፲፯
ዋቸው ፡ እነርሳቸው ፡ አይደሉምን ፡ ወንዶችም ፡
ያለ ፡ ሴት ፡ መኖር ፡ አይቻላቸውም ።
ምንም ፡ ብሩን ፡ ወርቁን ፡ መልካሙን ፡ ገንዘብ ፡ ፲፰
ሁሉ ፡ ቢሰበስቡ ፡ መልኳ ፡ ያማረ ፡ ደም ፡ ግባቷ ፡
የተወደደ ፡ አንዲት ፡ ሴትን ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ።
ያን ፡ ሁሉ ፡ ትተው ፡ እርሷን ፡ እርሷን ፡ ያያሉ ፡ ፲፱
ነገሯንም ፡ ይሰማሉ ፡ ሁሉም ፡ ምን ፡ ታምር ፡
እያሉ ፡ ያደንቃሉ ፡ ከወርቅና ፡ ከብር ፡ ከማረ
ውም ፡ ገንዘብ ፡ ሁሉ ፡ እርሷን ፡ ይመርጧታል ።
ልጅም ፡ ያሳደገውን ፡ አባቱን ፡ ትቶ ፡ አገሩንም ፡ ፳
ትቶ ፡ ሚስቱን ፡ ተከትሎ ፡ ይሄዳል ።
ስለ ፡ ሚስቱ ፡ ሰውነቱን ፡ ለመከራ ፡ አሳልፎ ፡ ፳፩
ይሰጣል ፡ አባት ፡ እናቱን ፡ አገሩንም ፡ አያስበ
ቸውም ።
ሴቶች ፡ እንዲያሸንፏችሁ ፡ በዚህ ፡ ታውቃላ ፳፪
ችሁ ፡ ጥራችሁ ፡ ግራችሁ ፡ ያመጣችሁትን ፡
ገንዘብ ፡ ሁሉ ፡ ለሴቶች ፡ የምትሰጧቸው ፡ አይ
ደላችሁምን ።
ሰው ፡ ጦሩን ፡ ይዞ ፡ ባሕሩን ፡ ዋኝቶ ፡ ወንዙን ፡ ፳፫
ተሻግሮ ፡ ሄዶ ፡ ይሰርቃል ።

፳፬፤ በጨለማም፡ይሄዳል፡አንበሳም፡ቢያይ፡ፈርቶ፡
አይመለስም ፡ በሰረቀም ፡ ጊዜ ፡ ሰርቆ ፡ ያመጣ
ውን ፡ ይሰጣታል ።
፳፭፤ ሰው ፡ ከወለዱት ፡ ከናቱና ፡ ከባቱ ፡ ሚስቱን ፡
ይወዳታል ።
፳፮፤ በሴቶች ፡ ምክንያት ፡ አእምሮአቸውን ፡ አጥ
ተው ፡ ተገዥ ፡ የሆኑ ፡ ሰዎች ፡ ብዙ ፡ ናቸው ፡
ስለነርሳቸውም ፡ ባሮች ፡ የሆኑ ፡ ብዙ ፡ ናቸው ።
፳፯፤ በሴቶችም ፡ ምክንያት ፡ ፈጽመው ፡ በድለው ፡
የሞቱ ፡ ብዙዎች ፡ ናቸው ።
፳፰፤ አሁንም ፡ የምናገረውን ፡ ነገር ፡ ካልተቀበላች
ሁኝ ፡ ንጉሥ ፡ በሚገዛው ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ የሚ
ፈራ ፡ አይደለምን ? አሕዛብስ ፡ ሁሉ ፡ በዩት ፡
ጊዜ ፡ ወደርሱ ፡ መቅረብን ፡ የሚፈሩ ፡ አይደለ
ምን ?
፳፱፤ እነሆ ፡ የንጉሡ ፡ ቁባት ፡ የከበረ ፡ የበርጠቄ ፡
ልጅ ፡ ኤጴሚን ፡ በንጉሡ ፡ ቀኝ ፡ ትቀመጣለች ።
፴፤ የንጉሡን ፡ ዘውድ ፡ ከራሱ ፡ ላይ ፡ አውርዳ ፡
በራሷ ፡ ላይ ፡ ትደፋለች ፡ የንጉሡንም ፡ ፊት ፡
ትመታዋለች ።
፴፩፤ ከዚህም ፡ ሁሉ ፡ ነገር ፡ ጋራ ፡ ንጉሥ ፡ አፏን ፡
ያያል ፡ ብትስቅ ፡ ይስቃል ፡ ብትቆጣም ፡ ትናገር ፡
ዘንድ ፡ ቍጣዋም ፡ ይበርድ ፡ ዘንድ ፡ ያቆላምጣ
ታል ።
፴፪፤ እናንተ ፡ ሰዎች ፡ እንዲህ ፡ የሚያደርጉ ፡ ሴቶች ፡
አያሸንፉምን ፡ አለ ።
፴፫፤ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ንጉሡና ፡ ሹማምንቱ ፡ ዓይን ፡
ለዓይን ፡ ተያዩ ፡ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ የጽድቅን ፡
ነገር ፡ ይናገር ፡ ጀመረ ።
፴፬፤ እናንተ ፡ ሰዎች ፡ ጽድቅ ፡ ሁሉን ፡ ድል ፡ የሚ
ነሣ ፡ አይደለምን ፡ ከሰማይ ፡ በታች ፡ ያለች ፡
ምድር ፡ ደግ ፡ ናት ፡ በቃል ፡ ኪዳኑ ፡ ጸንታ ፡
ትኖራለች ፡ ከምድር ፡ በላይ ፡ ያለ ፡ ሰማዩም ፡
ደግ ፡ ነው ፡ በቃል ፡ ኪዳኑ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፡
ፀሐይም ፡ ከምሥራቅ ፡ ተነሥቶ ፡ በምዕራብ ፡
ገብቶ ፡ ዙሮ ፡ በምሥራቅ ፡ ፈጥኖ ፡ ይመጣል ፡
በመስዕ ፡ በኩል ፡ ዙሮ ፡ በንዲት ፡ ቀን ፡ በምሥ
ራቅ ፡ በኩል ፡ ይወጣል ።
፴፭፤ እንዲህ ፡ የሚያደርግ ፡ ፀሐይ ፡ ታላቅ ፡ አይደለ
ምን ፡ ጽድቅ ፡ ግን ፡ ከዚህ ፡ ሁሉ ፡ በልጣ ፡ ታሸ
ንፋለች ።
፴፮፤ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ጽድቅን ፡ ይፈልጋታል ፡ ሰማይም ፡
በርሷ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፡ ሥራውም ፡ ሁሉ ፡
በርሷ ፡ ፈጽሞ ፡ ያልፋል ፡ እውነት ፡ ነገር ፡ በያዘ ፡
ሰው ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አይገኝም ።
፴፯፤ ወይን ፡ በደለኛ ፡ ነው ፡ ንጉሥ ፡ በደለኛ ፡ ነው ፡
ሴቶችም ፡ በደለኞች ፡ ናቸው ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡
በደለኛ ፡ ነው ፡ ሥራቸውም ፡ ሁሉ ፡ በደል ፡
ነው ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ በጽድቅ ፡ የለም ፡ እነዚህ ፡
ሁሉ ፡ በበደላቸው ፡ ይሞታሉ ።
፴፰፤ ጽድቅ ፡ ግን ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ ታሸንፋለች ፡ ሕይ
ወት ፡ ናት ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ፈጽማ ፡ ጸንታ ፡ ትኖ
ራለች ።
፴፱፤ በርሷ ፡ ዘንድ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ መለ
የት ፡ የሰውን ፡ ፊት ፡ አይቶ ፡ ማድላት ፡ የለም ፡
ነገር ፡ ግን ፡ ጽድቅ ፡ በሐሰት ፡ በክፉ ፡ ነገር ፡
በክፉ ፡ ሰውም ፡ አታድርበትም ፡ ሰውም ፡ ሁሉ ፡
ሥራዋን ፡ ይወዳል ።
ጽድቅ ፡ ያደረበት ፡ ሰው ፡ በፍርድ ፡ ጊዜ ፡ ፵፤
አሰት ፡ አይፈርድም ፡ እርሷም ፡ ድል ፡ ትነሣ
ለች ፡ መንግሥት ፡ ገናንነት ፡ ያለሙ ፡ ሁሉ ፡ አገ
ዛዝም ፡ በርሷ ፡ ይገኛል ፡ ጌትነት ፡ ገንዘቡ ፡ የሆነ ፡
እግዚአብሔር ፡ ይክበር ፡ ይመስገን ፡ ብሎ ፡ ዝም ፡
አለ ።
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ጽድቅ ፡ ደግ ፡ ፵፩፤
ናት ፡ ከሁሉ ፡ ትበልጣለች ፡ ፈጽማ ፡ ድል ፡ ትነ
ሣለች ፡ ብለው ፡ ተናገሩ ።
ንጉሡም ፡ ዘሩባቤልን ፡ የምትወደውን ፡ ፈጽ ፵፪፤
መህ ፡ ከተጻፈው ፡ ሁሉ ፡ ለምን ፡ አደርግልሃ
ለሁ ፡ አንተ ፡ አዋቂ ፡ ሆነሃልና ፡ በቆይታ ፡ ከኔ ፡
ጋራ ፡ ትቀመጣለህ ፡ የኔ ፡ ባለሟሌም ፡ ትሆና
ለህ ፡ አለው ።
እርሱም ፡ ንጉሡን ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ ትሠራት ፡ ፵፫፤
ዘንድ ።
በቢሎንን ፡ ያጠፉት ፡ ዘንድ ፡ በወደደ ፡ ጊዜ ፡ ፵፬፤
በዚያም ፡ ይመለስ ፡ ዘንድ ፡ በተሳለ ፡ ጊዜ ፡
ቂሮስ ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ የወሰደውን ፡ ንዋየ ፡ ቅድ
ሳቱንም ፡ ሁሉ ፡ ትመልስ ፡ ዘንድ ፡ በነገሥህ ፡
ጊዜ ፡ የተሳልከውን ፡ ስእለት ፡ አስብ ፡ አለው ።
የፋርስ ፡ ሰዎች ፡ ይሁዳን ፡ በጠፉት ፡ ጊዜ ፡ አይ ፵፭፤
ሁድ ፡ ያቃጠሏት ፡ ቤተ ፡ መቅደስን ፡ ትሠራ ፡
ዘንድ ፡ አንተም ፡ እንደ ፡ ተሳልክ ፡ አስተውል ።
አሁንም ፡ ጌታዬ ፡ ንጉሥ ፡ የምማልድህ ፡ የምለ ፵፮፤
ምንህ ፡ ይህ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ ካንተ ፡ የምፈልጋት ፡
ታላቅ ፡ ነገር ፡ ይቺ ፡ ናት ፡ ሰማይን ፡ ለፈጠረ ፡
ለእግዚአብሔር ፡ የተሳልከውን ፡ ስእለትክን ፡
ታደርግ ፡ ዘንድ ፡ ጌታዬ ፡ እሺ ፡ በለኝ ፡ ካንደበ
ትህ ፡ የወጣውንም ፡ ነገር ፡ ጨርስ ፡ አለው ።
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ንጉሡ ፡ ዳርዮስ ፡ ዘሩባቤልን ፡ ፵፯፤
አቅፎ ፡ ሳመው ፡ እርሱን ፡ ይሸኙት ፡ ዘንድ ፡
ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ያሉ ፡ ይሸኙት ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ኢየ
ሩሳሌምም ፡ የወጡ ፡ ሰዎችን ፡ ሁሉ ፡ ያሰናብቷ
ቸው ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ አለቆችና ፡ ወደ ፡ ራቅ ፡
ማሠሪያዎች ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ መኳንንትና ፡ ወደ ፡
ሹማምንቱም ፡ ደብዳቤዎችን ፡ ጻፈለት ።
ከርሱ ፡ ጋር ፡ ቤተ ፡ መቅደስን ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ፵፰፤
የዋንዛውን ፡ የዝግባውን ፡ እንጨት ፡ ወደ ፡ ኢየ
ሩሳሌም ፡ እንዲያመጡ ፡ በደጋ ፡ ላሉ ፡ ሰዎችና ፡
የሶርያ ፡ ክፍል ፡ በምትሆን ፡ ለሹማምንትም ፡
ሁሉ ፡ ደብዳቤ ፡ ጽፎ ፡ ሰደደላቸው ።
አርበኞቻቸው ፡ የሚሆኑ ፡ ባልንጀሮቻቸውን ፡ ፵፱፤
ሁሉ ፡ ከመገዛታቸው ፡ ነፃ ፡ ያወጧቸው ፡ ዘንድ ፡
በሚገዛው ፡ አገር ፡ ወደ ፡ ይሁዳ ፡ ለሚወጡ ፡
አይሁድ ፡ ሁሉ ፡ ጽፎ ፡ ደብዳቤ ፡ ሰደደላቸው ።
ከሹማምንቶቻቸውና ፡ ከራቅ ፡ ማሠሪያዎቻ ፶፤
ቸው ፡ ከመኳንንቶቻቸውም ፡ ሆኖ ፡ ወደ ፡ አደ
ባባያቸው ፡ ግብር ፡ እንዳያመጡ ፡ በውራጃቸው ፡
ላሉ ፡ ሰዎች ፡ ግብሩን ፡ ይፍቁላቸው ፡ ዘንድ ፡

አይሁድም ፡ አጽንተው ፡ የያዙትን ፡ በታቸውን ፡
ይተዉ ፡ ዘንድ ፡፡
፶፩ ሥራው ፡ እስኪፈጸም ፡ ድረስ ፡ ለቤተ ፡ መቅ
ደስ ፡ ሥራ ፡ የሚሆን ፡ በመት ፡ በመት ፡ ኻያ ፡
መክሊት ፡ ወርቅ ፡ ይሰጧቸው ፡ ዘንድ ፡ ደብ
ዳቤ ፡ ጽፎ ፡ ሰደደ ፡፡
፶፪ እንደ ፡ ሥራቱ ፡ እንደ ፡ ልማዳቸው ፡ በመሠዊ
ያው ፡ ዘወትር ፡ ለሚሠዉት ፡ መሥዋዕት ፡
በመት ፡ በመት ፡ አሥራ ፡ ሰባት ፡ መክሊት ፡
ዳግመኛም ፡ አሥር ፡ መክሊት ፡ ወርቅን ፡ ይሰ
ጧቸው ፡ ዘንድ ፡ ደብዳቤ ፡ ጽፎ ፡ ሰደደ ፡፡
፶፫ ቤተ ፡ መቅደስን ፡ ለመሥራት ፡ ከባቢሎን ፡ ወደ ፡
ኢየሩሳሌም ፡ የሚመጡትን ፡ ሁሉ ፡ ልጆቻቸ
ውንም ፡ ከመገዛት ፡ ነፃ ፡ ያወጧቸው ፡ ዘንድ ፡
ደብዳቤ ፡ ጽፎ ፡ ሰደደ ፡፡
፶፬ ለሚወጡ ፡ ከሀናት ፡ ሁሉ ፡ በሚሠሩ ፡ ገንዘብ ፡
የሥራ ፡ ልብሳቸውንና ፡ ምግባቸውን ፡ ይሰጧ
ቸው ፡ ዘንድ ፡ ጻፈላቸው ፡፡
፶፭ በኢየሩሳሌም ፡ ያለ ፡ የቤተ ፡ መቅደስ ፡ ሥራ ፡
እስኪፈጸም ፡ ድረስ ፡ ለሌዋውያንም ፡ ምግባቸ
ውን ፡ ይሰጧቸው ፡ ዘንድ ፡ ደብዳቤ ፡ ጽፎ ፡ ላከ
ላቸው ፡፡
፶፮ ለሚገዙ ፡ ቤተ ፡ መቅደስንም ፡ ለሚሠሩ ፡ ሁሉ ፡
ምግባቸውን ፡ ይሰጧቸው ፡ ዘንድ ፡ ጻፈላቸው ፡፡
፶፯ ቂሮስም ፡ ከባቢሎን ፡ ያወጣውን ፡ ንዋየ ፡ ቅድ
ሳቱን ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ላከላቸው ፡
ቂሮስ ፡ ሁሉን ፡ ያደርጉላቸው ፡ ዘንድ ፡ እንዳዘ
ዘላቸው ፡ ዳርዮስም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡
ይወጡ ፡ ዘንድ ፡ ልብሳቸውንና ፡ ቀለባቸውንም ፡
እንዲሰጧቸው ፡ አዘዛቸው ፡፡
፶፰ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ዘሩባቤል ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡
ኢየሩሳሌም ፡ አንፃር ፡ አንገቱን ፡ አንቅቶ ፡ ሰማ
ያትን ፡ የፈጠረ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰገነ ፡፡
፶፱ ድል ፡ መንሣት ፡ ካንተ ፡ ይገኛል ፡ ዕውቀትም ፡
ካንተ ፡ ይገኛል ፡ ጌትነትም ፡ ያንተ ፡ ገንዘብ ፡
ነው ፡ እኔም ፡ ያንተ ፡ ባሪያ ፡ ነኝ ፡፡
፷ ዕውቀትን ፡ የሰጠኸኝ ፡ አንተም ፡ የተመሰገንህ ፡
ነህ ፡ አቤቱ ፡ ጌታችን ፡ አባቶቻችንም ፡ ባንተ ፡
አመኑ ፡፡
፷፩ ደብዳቤውን ፡ ተቀብሎ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ሄደ ፡
ለወንድሞቹ ፡ ሁሉ ፡ ይኸንን ፡ ነገራቸው ፡፡
፷፪ ወጥተው ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ ይሠሩዋት ፡ ዘንድ ፡፡
፷፫ ስሙ ፡ የተጠራበት ፡ ቤተ ፡ መቅደስን ፡ ይሠ
ሯት ፡ ዘንድ ፡ ይቅር ፡ ብሎ ፡ ዕረፍትን ፡ የሰጣ
ቸው ፡ ያባቶቻቸውን ፡ ፈጣሪ ፡ አመሰገኑ ፡ መሰ
ንቆውን ፡ በገናውን ፡ እየመቱ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡
ተድላ ፡ ደስታ ፡ አደረጉ ፡፡

ምዕራፍ ፡ ፭ ፡፡

፩ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ የሚ
ወጡ ፡ ያባቶቻቸውን ፡ ወገኖች ፡ አለቆች ፡ በየ
ወገኖቻቸው ፡ ለዩ ፡ ሚስቶቻቸውን ፡ ሴቶች ፡
ልጆቻቸውንና ፡ ወንዶች ፡ ልጆቻቸውን ፡ ሴቶች ፡
ባሮቻቸውንና ፡ ወንዶች ፡ ባሮቻቸውን ፡ ከብቶ
ቻቸውንም ፡ ለዩ ፡፡
፪ ዳርዮስም ፡ መሰንቆውን ፡ በገናውን ፡ ከበሮውን ፡
እየመቱ ፡ በተድላ ፡ በደስታ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ያደ
ርሷቸው ፡ ዘንድ ፡ ከነርሱቸው ፡ ጋራ ፡ ሺ ፡ ፈረ
ሰኛ ፡ ሰደደ ፡፡
፫ ወንድሞቻቸውም ፡ ሁሉ ፡ ከነርሱ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡
ሆነው ፡ እየዘፈኑም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወጡ ፡፡
፬ በየሀገራቸው ፡ በየወገናቸው ፡ በየሹመታቸው ፡
አውራጃ ፡ የወጡ ፡ ያለቆች ፡ ስማቸው ፡ ይህ ፡
ነው ፡፡
፭ የአሮን ፡ ልጆችና ፡ የፊንሐስ ፡ ልጆች ፡ የወጡ ፡
የሆኑ ፡ ካህናት ፡ ስም ፡ ይህ ፡ ነው ፡ አንዱ ፡
የሰራሀዩ ፡ ልጅ ፡ የኢዮሴዴቅ ፡ ልጅ ፡ ኢዮስ
ያስ ፡ ነው ፡ ሁለተኛውም ፡ የሰላትያል ፡ ልጅ ፡
የዘሩባቤል ፡ ልጅ ፡ ኢዮአቄም ፡ ነው ፡ ለሰላት
ያል ፡ የይሁዳ ፡ ወገን ፡ ከሚሆን ፡ ከፋሬስ ፡ ወገን ፡
ከሚሆን ፡ ከዳዊት ፡ ወገን ፡ የተወለደ ፡ ብሎ ፡
ቀጸለለት ፡፡
፮ በነገሠ ፡ በሁለተኛው ፡ ዘመን ፡ በመጀመሪያ ፡
ወር ፡ በሚያገዛ ፡ በፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ በዳርዮስ ፡
ፊት ፡ የጥበብን ፡ ነገር ፡ የተናገረ ፡ ዘሩባቤል ፡
ነው ፡፡
፯ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆር ፡ ከማረካቸው ፡
ከፋርስ ፡ ምርኮ ፡ ተለይተው ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳ
ሌም ፡ የወጡ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ ያገቧ
ቸው ፡ ከነገደ ፡ ይሁዳ ፡ ወገን ፡ የሚሆን ፡ ሰዎች ፡
እሊህ ፡ ናቸው ፡፡
፰ ወደ ፡ ይሁዳም ፡ የገቡ ፡ ሰዎች ፡ እሉ ፡ ሁሉንም ፡
በያገሮቻቸው ፡ ሰደዷቸው ፡ ከኢዮስያስና ፡ ከዘ
ሩባቤል ፡ ጋራ ፡ ሄዱ ፡ ኢዮስያስ ፡ የነሂምዩ ፡ ልጅ ፡
ነው ፡ ነሂምዩ ፡ የዛሬዳ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ ዛሬዳ ፡ የሬ
ስዩ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ ሬስዩ ፡ የሔኔዩስ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡
ሔኔዩስ ፡ የመርዶክዮስ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ መርዶክ
ዮስ ፡ የብኤልሰር ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ ብኤልሰር ፡ የአ
ስፈራስ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ አስፈራስ ፡ የቤሮልዩ ፡
ልጅ ፡ ነው ፡ ቤሮልዩ ፡ የራሂሙ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡
ራሂሙ ፡ የባዓና ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ እሊህ ፡ ሁሉ ፡
አስቀድመው ፡ የተሾሙላቸው ፡ የሹማምንት ፡
ልጆች ፡ ናቸው ፡፡
፱ ከሕዝቡ ፡ የተቈጠሩ ፡ የፋሬስ ፡ ልጆች ፡ በቍጥ
ራቸው ፡ ሰባት ፡ እልፍ ፡ ከሁለት ፡ ሺ ፡ ካንድ ፡
መቶ ፡ ሰባ ፡ ሁለት ፡ ናቸው ፡ የሳፋንም ፡ ልጆች ፡
ሦስት ፡ መቶ ፡ ሰባ ፡ ሁለት ፡ ናቸው ፡፡
፲ የሐሬስ ፡ ልጆችም ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ሃምሳ ፡
ሰባት ፡ ናቸው ፡፡
፲፩ የአትሊ ፡ ሞዓብ ፡ ልጆችም ፡ ከዘሩከብሊና ፡ ከኢ
ዮስያስ ፡ ልጆች ፡ ጋራ ፡ በቍጥራቸው ፡ ሁለት ፡
ሺ ፡ ስምንት ፡ መቶ ፡ ሁለት ፡ ናቸው ፡፡
፲፪ የዮሳም ፡ ልጆች ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ናቸው ፡ የዘጠ
ንም ፡ ልጆች ፡ ዘጠኝ ፡ መቶ ፡ ከስልሳ ፡ ናቸው ፡
የክሮባን ፡ ልጆች ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ ናቸው ፡
የባኒን ፡ ሰደቅ ፡ ልጆችም ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ አርባ ፡
ስምንት ፡ ናቸው ፡፡
፲፫ የበቤ ፡ ልጆችም ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ አራት ፡

ናቸው ፡ የሐርጊ ፡ ልጆችም ፡ ሺ ፡ ከራት ፡ መቶ ፡
ኻያ ፡ አራት ፡ ናቸው ።
፲፬፤ የአዶኒቂም ፡ ልጆችም ፡ ሠላሳ ፡ ዘጠኝ ፡ ናቸው ፡
የበሊን ፡ ልጆችም ፡ ሁለት ፡ ሺ ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡
ሦስት ፡ ናቸው ፡ የአዲስድም ፡ ልጆች ፡ አራት ፡
መቶ ፡ ሃምሳ ፡ አራት ፡ ናቸው ።]
፲፭፤ የአዝራቂዩ ፡ የቂሳን ፡ የአዛጦን ፡ ልጆች ፡ ስሳ ፡
ሰባት ፡ ናቸው ፡ የአዘሩ ፡ ልጆችም ፡ መቶ ፡
ሠላሳ ፡ ሁለት ፡ ናቸው ።
፲፮፤ የሐናንያም ፡ ልጆች ፡ መቶ ፡ አራት ፡ ናቸው ፡
የአሮምና ፡ የበሕሲም ፡ ልጆች ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡
ኻያ ፡ ሦስት ፡ ናቸው ።
፲፯፤ የአርስፋስት ፡ የበጢሩስ ፡ ልጆችም ፡ ሦስት ፡
መቶ ፡ ከምስት ፡ ናቸው ፡ የኤናውም ፡ ልጆች ፡
መቶ ፡ ሃምሳ ፡ ስምንት ፡ ናቸው ፡ የዓቃቢሃ ፡
ተሎሞንም ፡ ልጆች ፡ መቶ ፡ ኻያ ፡ ሦስት ፡
ናቸው ።
፲፰፤ የኒጤቤንም ፡ ልጆች ፡ አምሳ ፡ አምስት ፡ ናቸው ።
፲፱፤ የሞተው ፡ የቢጠርሞንና ፡ የቀቃርቲ ፡ ሐርዮስ ፡
ልጆችም ፡ ኻያ ፡ አምስት ፡ ናቸው ፡ የጾሬስ ፡
ፎርግም ፡ ልጆች ፡ ሰባት ፡ መቶ ፡ ናቸው ።
፳፤ የብድያስ ፡ የአውሚዳውያንም ፡ ልጆች ፡ አራት ፡
መቶ ፡ ኻያ ፡ ሁለት ፡ ናቸው ፡ የአቍሬ ፡ መስቃ
ቢስም ፡ ልጆች ፡ ስድስት ፡ መቶ ፡ ኻያ ፡ አንድ ፡
ናቸው ።
፳፩፤ የመቃሎንም ፡ ልጆች ፡ መቶ ፡ ኻያ ፡ ሁለት ፡
ናቸው ፡ የቤጠቢዎንም ፡ ልጆች ፡ አምሳ ፡
ሁለት ፡ ናቸው ፡ የኔፋስም ፡ ልጆች ፡ መቶ ፡
አምሳ ፡ ስድስት ፡ ናቸው ።
፳፪፤ የሁነሰና ፡ የቀላምሉም ፡ ልጆች ፡ ስድስት ፡
መቶ ፡ ኻያ ፡ አምስት ፡ ናቸው ።
፳፫፤ የሰናሐስም ፡ ልጆች ፡ ሦስት ፡ ሺ ፡ ከሦስት ፡
መቶ ፡ አንድ ፡ ናቸው ።
፳፬፤ የኢዮስያስ ፡ ልጆች ፡ ከህናቱም ፡ ከሰናብ ፡ ልጆች ፡
ጋራ ፡ ስምንት ፡ መቶ ፡ ሰባ ፡ ሁለት ፡ ናቸው ።
የኤምሩት ፡ ልጆችም ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡
ሁለት ፡ ናቸው ።
፳፭፤ የፋሰሩ ፡ ልጆችም ፡ ሺ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ አርባ ፡
ሰባት ፡ ናቸው ።
፳፮፤ የኢዮስያስ ፡ የዛቆዲኤሉ ፡ የበኑና ፡ የሱድይ ፡
ልጆች ፡ ሌዋውያን ፡ ግን ፡ ሰባ ፡ አራት ፡ ናቸው ።
፳፯፤ ግናያቱን ፡ የሚያደርሱ ፡ የአሳፍ ፡ ልጆች ፡ ካህ
ናቱም ፡ መቶ ፡ ኻያ ፡ ስምንት ፡ ናቸው ።
፳፰፤ የቤተ ፡ መቅደስን ፡ በር ፡ የሚዘጉ ፡ እስማኤላ
ውያን ፡ አራት ፡ መቶ ፡ ናቸው ፡ የኔሮወጣማን ፡
ልጆች ፡ የደቀበውና ፡ የማዕ ፡ ልጆችም ፡ ሺ ፡
ናቸው ፡ የጢኪስ ፡ ልጆችም ፡ ሁሉ ፡ መቶ ፡
ኻያ ፡ ዘጠኝ ፡ ናቸው ።
፳፱፤ የኤሳው ፡ ልጆችና ፡ የካህናቱ ፡ ልጆት ፡ የጠቢ
ሎት ፡ የጋፍ ፡ ልጆች ፡ የሱህ ፡ ልጆች ፡ የቀራስ ፡
ልጆች ፡ የፋሌድ ፡ ልጆች ፡ የሊበና ፡ ልጆች ።
፴፤ የሐቁድ ፡ ልጆች ፡ የአቢጋ ፡ ልጆች ፡ የቴግብ ፡
ልጆች ፡ የሐጡ ፡ ልጆች ፡ የዓቀብ ፡ ልጆች ፡
የሰባዊ ፡ ልጆች ፡ የቂን ፡ ልጆች ፡ የሐና ፡ ልጆች ።

የሐዳር ፡ ልጆች ፡ የያሰሩ ፡ ልጆች ፡ የናሔበ ፡ ፴፩፤
ልጆች ፡ የዱሳን ፡ ልጆች ፡ የከሊባ ፡ ልጆች ፡
የቀዚራ ፡ ልጆች ፡ የአዚሩ ፡ ልጆች ፡ የፋኑሕ ፡
ልጆች ፡ የቤሴቲ ፡ ልጆች ፡ የአበሬን ፡ ልጆች ፡
የቤሕቲ ፡ ልጆች ፡ የሐሰና ፡ ልጆች ፡ የማኒ ፡
ልጆች ፡ የፋናሲ ፡ ልጆች ፡ የአቂፋ ፡ ልጆች ፡
የአኬብ ፡ ልጆች ፡ የአሶር ፡ ልጆች ፡ የፋርቂም ፡
የበስሊም ፡ ልጆች ።
የይዳ ፡ ልጆች ፡ የበኩስ ፡ ልጆች ፡ የሲሬር ፡ ፴፪፤
ልጆች ፡ የቶብሔ ፡ ልጆች ፡ የናሲ ፡ ልጆች ፡
የአጣፍ ፡ ልጆች ።
የሰሎሞን ፡ የልጅ ፡ ልጆች ፡ የአሰፍያት ፡ ልጆች ፡ ፴፫፤
የፋሬዳ ፡ ልጆች ፡ የሐሊና ፡ ልጆች ፡ የሎዝን ፡
ልጆች ፡ የያሴዳሔል ፡ ልጆች ፡ የሳሌ ፡ ልጆች ።
የሐጋያ ፡ ልጆች ፡ የፈቀሬ ፡ ተሰባይ ፡ ልጆች ፡ ፴፬፤
የጠፎፎትዮ ፡ ልጆች ፡ የመሲጣስ ፡ ልጆች ፡
የጋሊ ፡ ልጆች ፡ የአዲስ ፡ ልጆች ፡ የሰቢስ ፡
ልጆች ፡ የአፊራ ፡ ልጆች ፡ የደሩዲስ ፡ ልጆች ፡
የሰፈማ ፡ ልጆች ።
ካህናቱን ፡ የሚያገለግሉ ፡ የሌሎች ፡ ልጆች ፡ ፴፭፤
ሁሉ ፡ የሰሎሞንም ፡ የልጅ ፡ ልጆቹ ፡ እነዚህ ፡
ሁሉ ፡ አራት ፡ ሺህ ፡ ሰባ ፡ ሁለት ፡ ናቸው ።
ከፋርስና ፡ ከሕንድም ፡ የወጡት ፡ ሁሉ ፡ እኒህ ፡ ፴፮፤
ናቸው ፡ አለቆቻቸውም ፡ ከራኅታንና ፡ ሀለር ፡
ናቸው ።
ከእስራኤል ፡ ወገን ፡ የሚሆኑ ፡ እሊህ ፡ አገራቸ ፡ ፴፯፤
ውን ፡ ዘመዳቸውን ፡ መናገር ፡ አልተቻላቸ
ውም ፡ የውባን ፡ ልጅ ፡ የዱዳን ፡ የነቆዲንም ፡
ልጆች ፡ ዘጠኝ ፡ ሺህ ፡ ሐምሳ ፡ ሁለት ፡ ናቸው ።
ከካህናቱ ፡ የተወለዱ ፡ የክህነታቸውን ፡ ሥራ ፡ ፴፰፤
የሚሠራ ፡ የትውልዳቸው ፡ ቍጥር ፡ አልተገ
ኘም ፡ የሐብያ ፡ ልጆች ፡ የኢያዕቅበስ ፡ ልጆች ፡
እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ በቍጥራቸው ፡ አልተገኙም ።
ከፊርዘሌው ፡ ልጆች ፡ ወገን ፡ የምትሆን ፡ አው
ግያን ፡ ያገባ ፡ የይሆድሰም ፡ ልጆች ፡ ቍጥር ፡
አልተገኘም ፡ በስሙም ፡ ተጠራች ።
የዘመዶቹም ፡ ትውልድ ፡ ቍጥር ፡ ከተጻፈበት ፡ ፴፱፤
መጽሐፍ ፡ ትውልዱን ፡ ፈልገው ፡ ቢያጡ ፡
ከሹመቱ ፡ ሻሩት ።
እውነት ፡ ነገር ፡ የማለማበት ፡ ልብሰ ፡ ተክህኖ ፡ ፵፤
የሚለብስ ፡ ሊቀ ፡ ካህናት ፡ እስቲሾሙ ፡ ድረስ ፡
ተረፈ ፡ መሥዋዕቱን ፡ እንዳይሰጡት ፡ ኢታር
ያና ፡ ነሐምያ ፡ አዘዙዋቸው ።
ከሥራ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ በላይ ፡ ያሉት ፡ እስራ ፡ ፵፩፤
ኤል ፡ ሁሉ ፡ ከሴቶች ፡ ባሮቻቸውና ፡ ከወን
ዶች ፡ ባሮቻቸው ፡ በቀር ፡ አራት ፡ እልፍ ፡ ከሁ
ለት ፡ ሺ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ናቸው ።
ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ባሮቻቸውም ፡ ሰባት ፡ ሺህ ፡ ፵፪፤
ከሦስት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ሰባት ፡ ናቸው ፡ ሴቶ
ችና ፡ ወንዶች ፡ አመስጋኞችም ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡
አርባ ፡ አምስት ፡ ናቸው ።
ግመሎቹም ፡ አራት ፡ መቶ ፡ አርባ ፡ ስድስት ፡ ፵፫፤
ናቸው ፡ ፈረሶቹም ፡ ሰባት ፡ ሺ ፡ ከሦስት ፡ መቶ ፡
አርባ ፡ ስድስት ፡ ናቸው ፡ በቅሎችም ፡ ሁለት ፡

መቶ ፡ አርበ ፡ አምስት ፡ ናቸው ፡ አህዮችም ፡ አምስት ፡ ሺ ፡ ከምስት ፡ መቶ ፡ ኻያ ፡ አምስት ፡ ናቸው ።

፵፬ ከያቶቻቸው ፡ አለቆች ፡ ወገን ፡ ሁሉ ፡ ተጨምረው ፡ ተቈጥረው ፡ ይህን ፡ ያህል ፡ ናቸው ፡ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ወዳለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደሚመሰገንበት ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ በደረሱ ፡ ጊዜ ፡ እንደሚቻላቸው ፡ መጠን ፡ ቤተ ፡ መቅደስን ፡ በጥንቱ ፡ ቦታ ፡ ይሠሩት ፡ ዘንድ ።

፵፭ ለቤተ ፡ መቅደስ ፡ ሊሠሩበት ፡ ጥቃቅን ፡ ዕቃ ፡ የተሳሉትን ፡ ሺ ፡ ወቄት ፡ ወርቅ ፡ አምስት ፡ ሺ ፡ ወቄትም ፡ ብር ፡ መቶ ፡ ልብሰ ፡ ተክህኖም ፡ ወደ ፡ ምጽዋቱ ፡ ዕቃ ፡ ያገቡ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ አመለከቱ ።

፵፮ ካህናቱም ፡ ሌዋውያንም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ካሉ ፡ ወገኖች ፡ የሚሆኑ ፡ ሰዎችም ፡ ግናያቱን ፡ የሚያደርሱ ፡ በሩንም ፡ የሚዘጉ ፡ ሰዎች ፡ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ በየቦታቸው ፡ ይቀመጡ ፡ ነበር ።

፵፯ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በየገራቸው ፡ ተቀምጠው ፡ ሳሉ ፡ በሰባተኛው ፡ ወር ፡ መባቻ ፡ በምሥራቁ ፡ በር ፡ ዳርቻ ፡ ባለው ፡ አደባባይ ፡ ተሰበሰቡ ።

፵፰ የዮሴዴቅ ፡ ልጆች ፡ ኢዮስያስ ፡ አገልጋዮች ፡ የሚሆኑ ፡ ወንድሞቹ ፡ የሰላትያል ፡ ልጅ ፡ ዘሩባቤልም ፡ ተቀመጡ ።

፵፱ ወንድሞቹ ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ወገን ፡ በሚሆን ፡ በሙሴ ፡ መጽሐፍ ፡ እንደተጻፉ ፡ እንደ ፡ ሕጉ ፡ እንደ ፡ ሥርዓቱ ፡ መሥዋዕት ፡ ይሠዉ ፡ ዘንድ ፡ ለእስራኤል ፡ ፈጣሪ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መሠዊያውን ፡ አዘጋጁለት ።

፶ ልዩ ፡ የሚሆኑ ፡ ባላገሮችም ፡ ከነርሱ ፡ ጋራ ፡ ተሰብስበው ፡ በየቦታቸው ፡ በምሥዋዑ ፡ አጠገብ ፡ ተዘጋጁ ፡ ተሰልፈው ፡ ነበርና ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ባላገሮችን ፡ አጠኗቸው ፡ በየጊዜው ፡ የሚደረገውን ፡ የነግሁንና ፡ የሠርኩን ፡ መሥዋዕቱን ፡ ቍርባኑን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አቀረቡ ።

፶፩ በአሪት ፡ እንደተጻፈ ፡ ዘለሳ ፡ ጥለው ፡ በዓል ፡ አደረጉ ፡ ሁለጊዜም ፡ እንደ ፡ ቀደመው ፡ መሥዋዕቱን ፡ ሠዉ ።

፶፪ ዳግመኛም ፡ የዘወትሩን ፡ ቍርባን ፡ አቀረቡ ፡ ቅዳሜ ፡ ቅዳሜ ፡ የሚሠዉትን ፡ የመባቻውንም ፡ መሥዋዕት ፡ አቀረቡ ፡ ሁለጊዜ ፡ የሚደረጉ ፡ በዓላትንም ፡ ለዩ ።

፶፫ ለእግዚአብሔር ፡ ስለት ፡ የተሳሉ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ከሰባተኛው ፡ ወር ፡ መባቻ ፡ በኋላ ፡ መሥዋዕቱን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ያቀርቡ ፡ ጀመሩ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ግን ፡ ገና ፡ አልተሠራም ፡ ነበር ።

፶፬ ደንጊያ ፡ ለሚያለዝቡ ፡ እንጨትም ፡ ለሚጠርቡ ፡ ሰዎች ፡ ቀለባቸውን ፡ ብሩን ፡ ወርቁን ፡ መብሉንም ፡ መጠጡንም ፡ ሰጧቸው ።

፶፭ የሲዶናን ፡ ሰዎች ፡ የጢሮስንም ፡ ሰዎች ፡ የቀንዛውን ፡ የዝግባውን ፡ እንጨቶች ፡ ከዶጋ ፡ ኢዮጴ ፡ በሚባል ፡ ባሕር ፡ መርከብ ፡ ያገቡላቸው ፡ ዘንድ ፡ አዘዟቸው ፡ ከፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ ከቂሮስ ፡ ዘንድም ፡ የትእዛዝ ፡ ደብዳቤን ፡ ጻፉላቸው ።

፶፮ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ በደረሱ ፡ ጊዜ ፡ በሁለተኛው ፡ ዓመት ፡ በሁለተኛው ፡ ወር ፡ የሰላትያል ፡ ልጅ ፡ ዘሩባቤል ፡ የኢዮሴዴቅ ፡ ልጅ ፡ ኢዮስያስ ፡ ወንድሞቻቸውም ፡ ካህናቱ ፡ ሌዋውያንም ፡ ተማርከው ፡ ከኼዱበት ፡ አገር ፡ ተመልሰው ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ የገቡትም ፡ ሁሉ ፡ ቤተ ፡ መቅደስን ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ጀመሩ ።

፶፯ ወደ ፡ ይሁዳና ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ በገቡ ፡ በሁለተኛው ፡ ዘመን ፡ በሁለተኛው ፡ ወር ፡ የእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ሠሩ ።

፶፰ ሌዋውያንንም ፡ በቤተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሥራ ፡ ላይ ፡ ሾሟቸው ፡ ልጆቹና ፡ ኢዮስያስ ፡ ወንድሞቹም ፡ ወንድሙም ፡ የሚሆን ፡ አድያምያልሂም ፡ ተሾሙ ፡ የኢዮስያስ ፡ ልጅ ፡ ኄሜዳቦን ፡ የኤልያደን ፡ ልጅ ፡ የይሁዳ ፡ ልጅ ፡ ከልጆቹ ፡ ከወንድሞቹም ፡ ጋራ ፡ ተሾሙ ፡ ሌዋውያንም ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ የቤተ ፡ መቅደስን ፡ ሥራ ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ የሥራ ፡ አለቆች ፡ ሆነው ፡ አንድነት ፡ ተሾሙ ።

፶፱ ካህናቱም ፡ ልብሰ ፡ ተክህኖውን ፡ ለብሰው ፡ መሰንቆውንና ፡ መለከቱን ፡ ይዘው ፡ ቆሙ ፡ የአሳፍ ፡ ልጆች ፡ ሌዋውያንም ፡ ጸናጽል ፡ እየመቱ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመሰግኑ ፡ ነበር ።

፷ የዕሜይ ፡ ልጅ ፡ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊትን ፡ በገና ፡ እየደረደሩ ፡ ያመሰግኑት ፡ ነበር ።

፷፩ ምስጋናውንም ፡ እየጮኹ ፡ ያመሰግኑ ፡ ነበር ፡ ምስጋናው ፡ ለዘላለሙ ፡ ነውና ፡ ቸርነቱም ፡ ለእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ነውና ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመሰግኑ ፡ ነበር ።

፷፪ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ቀንደ ፡ መለከቱን ፡ እየነፉ ፡ ቃላቸውን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አድርገው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ በታደሰች ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰገኑት ።

፷፫ ቀድሞ ፡ በዚያ ፡ በየገራቸው ፡ ይኖሩ ፡ የነበሩ ፡ ከካህናት ፡ ወገን ፡ የሚሆኑ ፡ ሌዋውያንም ፡ መጡ ፡ የዚያን ፡ ቤት ፡ ሥራውን ፡ ቀድሞ ፡ ያውቁት ፡ የነበሩ ፡ አለቆችም ፡ በታላቅ ፡ ቃል ፡ ፈጽመው ፡ እያለቀሱ ፡ መጡ ።

፷፬ ሕዝቡም ፡ እስኪሰሙ ፡ ድረስ ፡ ቀንደ ፡ መለከት ፡ እየነፉ ፡ ደስ ፡ ያላቸው ፡ ሰዎች ፡ ብዙ ፡ ነበሩ ።

፷፭ ከሩቅ ፡ እስኪሰማ ፡ ድረስ ፡ በታላቅ ፡ ድምፅ ፡ ቀንደ ፡ መለከቱን ፡ የሚነፉ ፡ ሰዎች ፡ ብዙ ፡ ነበሩና ፡ ምንም ፡ ቢበዙ ፡ ከሕዝቡም ፡ ልቅሶ ፡ የተነሣ ፡ ቀንደ ፡ መለከቱን ፡ ድምፅ ፡ አልሰሙም ።

፷፮ የብንያምና ፡ የይሁዳ ፡ ወገኖች ፡ ጠላቶች ፡ የቀንደ ፡ መለከቱን ፡ ድምፅ ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ያ ፡ የቀንደ ፡ መለከቱ ፡ ድምፅ ፡ ምንም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ፡ መጡ ።

፷፯ ከተማረኩበት ፡ ከባቢሎን ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡

ተመለሱ፡እስራኤል፡የፈጣሪያቸው፡የእግዚአብሔርን፡ቤተ፡መቅደስ፡እንዲሠሩ፡በወቄ፡ጊዜ።
፷፰፤ ወደ፡ዘሩባቤል፡ወደ፡ኢዮስያስ፡አገራቸውንም፡ወደሚገዙ፡ሹማምንት፡ሄደው፡እኛም፡እንደ፡እናንተ፡ለፈጣሪያችሁ፡እንገዛለንና።
፷፱፤ ስልምናሶር፡ማርኮ፡ወደዚህ፡ከመጣን፡ጀምሮ፡መሥዋዕቱን፡ለርሱ፡እንሠዋለንና፡ከናንተ፡ጋራ፡እንሥራ፡አሏቸው።
፸፤ ዘሩባቤል፡ኢዮስያስም፡በገራቸው፡የተሾሙ፡ሹማምትም፡የእስራኤል፡ፈጣሪ፡የእግዚአብሔር፡ማደሪያ፡ቤተ፡መቅደስ፡መሥራት፡ለእኛ፡ለእናንተም፡አይገባንም፡አሏቸው።
፸፩፤ ነቢዩ፡ሐጌ፡እንደ፡ተናገረ፡የፋርስ፡ንጉሥ፡ቂሮስም፡እንዳዘዘን፡የእስራኤል፡ፈጣሪ፡የእግዚአብሔርን፡ቤተ፡መቅደስ፡እኛ፡ለብቻችን፡እንሠራለን፡እንጂ፡ከናንተ፡ጋራ፡ልንሠራ፡አይገባንም፡አሏቸው።
፸፪፤ የሚወረውሩ፡የሚመክቱ፡በገሩ፡ያሉ፡አኛም፡ከንቱ፡ግን፡በይሁዳ፡ያሉ፡እስራኤልን፡ፈጽመው፡ተሰብስበው፡ተዋጓቸው።
፸፫፤ አወኳቸው፡ሥራቸውንም፡አስቀሩ፡በንጉሥ፡በቂሮስ፡ዘመን፡ሁሉ፡እንዳይሠሩ፡ከለከሏቸው፡ዳርዮስም፡እስከ፡ነገሠበት፡እስከ፡ሁለተኛው፡ዓመት፡ድረስ፡እንዳይሠሩ፡ሥራውን፡ከለከሏቸው።

ምዕራፍ፡፮።

፩፤ ዳርዮስ፡በነገሠ፡በሁለተኛው፡ዘመን፡የሐዶ፡ልጅ፡ዘካርያስና፡ሐጌ፡ነቢያት፡በይሁዳና፡በኢየሩሳሌም፡ባሉ፡አይሁድ፡ላይ፡የእስራኤልን፡ፈጣሪ፡የእግዚአብሔርን፡ስም፡ጠርተው፡ትንቢት፡ተናገሩባቸው።
፪፤ ከዚህም፡በኋላ፡የሰላትያል፡ልጅ፡ዘሩባቤል፡የዮሴዴቅ፡ልጅ፡ኢዮስያስ፡ተነሡ፡ይረዷቸው፡ዘንድ፡እግዚአብሔር፡የሾማቸው፡ነቢያት፡አብረዋቸው፡ሳሉ፡በኢየሩሳሌም፡ያለ፡የእግዚአብሔርን፡ማደሪያ፡ቤተ፡መቅደስ፡ይሠሩ፡ጀመር።
፫፤ በነዚያም፡ወራቶች፡ፊንቂስና፡የሶርያ፡አለቃ፡ሲሳኒስ፡ሳሬታርዚኒስም፡አብረዋቸው፡ከባልንጀሮቻቸው፡ጋራ፡ወደነርሱ፡መጥተው።
፬፤ ይህንን፡ቤተ፡መቅደስ፡ትሠሩ፡ዘንድ፡ይህንንስ፡የቤተ፡መቅደስ፡ሥራ፡ሁሉ፡ደፍናችሁ፡ትሠሩት፡ዘንድ፡ማን፡አዘዛችሁ፡የሚሠሩትስ፡ሠራተኞች፡እነማናቸው።
፭፤ ይቅር፡ብሏቸዋልና፡ያን፡ጊዜ፡ለአይሁድ፡ሽማግሎች፡እግዚአብሔር፡በለሟልነትን፡ሰጣቸው።
፮፤ ወደ፡ዳርዮስ፡እስኪልኩ፡ደብዳቤንም፡እስኪያመጡላቸው፡ድረስ፡ሥራውን፡አልከለከሏቸውም።
፯፤ የፊንቂስና፡የሶርያ፡አለቃ፡ሲሳኒስ፡አስተረቡዛንስ፡በሶርያ፡በፊንቂስ፡ከነርሳቸው፡ጋራ፡አሉ፡ከሹማምንቱ፡ከባልንጀሮቻቸውም፡ጋራ፡ለንጉሡ፡ለዳርዮስ፡ትድረስ፡ብለው፡ወደ፡ዳርዮስ፡ጽፈው፡ላኩ።
ጌታችን፡ንጉሥ፡ሆይ፡ሁሉን፡ታውቅ፡ዘንድ፡ወደ፡ይሁዳ፡ወደ፡ኢየሩሳሌምም፡በመጣን፡ጊዜ፡የአይሁድን፡ምርኮኞች፡አለቆቻቸውንም፡በኢየሩሳሌም፡አገኘናቸው። ፰፤
በተቀረፀ፡ዋጋው፡ብዙ፡በሆነ፡ደንጊያ፡በየወገናቸው፡ማዕዘን፡ባላቸው፡እንጨቶችም፡የገነነ፡የታደሰ፡የእግዚአብሔር፡ማደሪያ፡ቤተ፡መቅደስን፡ሲሠሩ፡አገኘናቸው። ፱፤
ሲሠሩም፡ሥራውን፡ቸኩለው፡ይሠሩ፡ነበር፡በጃቸው፡እያፋጠኑ፡ተግተው፡ይሠሩ፡ነበር። ፲፤
ከዚህም፡በኋላ፡ይህንን፡ቤተ፡መቅደስን፡ትሠሩ፡ዘንድ፡ማን፡አዘዛችሁ፡ብለን፡ጠየቅናቸው። ፲፩፤
ሰዎቻቸውን፡በሥራቸው፡የትሾሙ፡አለቆችንም፡በየስማቸው፡ወዳንተ፡ጽፈን፡እንሰድ፡ዘንድ፡መረመርናቸው፡አለቆቻቸውንም፡ጠየቅናቸው። ፲፪፤
እኛስ፡ምድርንና፡ሰማይን፡የፈጠረ፡የእግዚአብሔር፡ባሮች፡ነን፡ብለው፡መለሱልን። ፲፫፤
ከብዙ፡ዘመን፡አስቀድሞ፡የእስራኤልን፡ንጉሥ፡ሰሎሞን፡አጽንቶ፡ደግ፡አድርጎ፡ፈጽሞ፡የሠራውን፡ይህን፡ቤተ፡መቅደስን፡ሠሩት። ፲፬፤
አባቶቻችን፡ኃጢአት፡ሠርተው፡የእስራኤልን፡ፈጣሪ፡አሳዝነውታልና፡በባቢሎን፡ንጉሥ፡በናቡከደነፆር፡እጅ፡በፋርስም፡ንጉሥ፡በስልምናሶር፡እጅ፡ጣላቸው። ፲፭፤
ይኸንንም፡ቤተ፡መቅደስ፡አፈረሰ፡በእሳትም፡አቃጠለ፡ሕዝቡንም፡ማርኮ፡ወደ፡ባቢሎን፡ወሰዳቸው። ፲፮፤
ቂሮስ፡በባቢሎን፡በነገሠ፡በመጀመሪያው፡ዘመን፡ንጉሡ፡ቂሮስ፡ይህን፡ቤተ፡መቅደስ፡ይሠሩ፡ዘንድ፡አዘዘ። ፲፯፤
ናቡከደነፆር፡በኢየሩሳሌም፡ካለው፡ቤተ፡መቅደስ፡ያወጣውን፡በዳራሹም፡ያኖረውን፡ብርና፡ወርቅ፡የሆነ፡ንዋየ፡ቅድሳቱን፡ዳግመኛ፡የፋርስ፡ንጉሥ፡ቂሮስ፡በባቢሎን፡ካለ፡ከዳራሹ፡አውጥቶ፡ለአለቃው፡ለአንበሮስና፡ለዘሩባቤል፡ሰጣቸው። ፲፰፤
ይኸንንም፡ንዋየ፡ቅድሳት፡ወስደው፡በኢየሩሳሌም፡ባለ፡ቤተ፡መቅደስ፡ያኖሩት፡ዘንድ፡የእግዚአብሔርንም፡ማደሪያ፡ቤተ፡መቅደስንም፡በበታው፡ይሠሩት፡ዘንድ፡አዘዛቸው። ፲፱፤
ከዚህም፡በኋላ፡አንበብሮስ፡ወደ፡ኢየሩሳሌም፡በደረሰ፡ጊዜ፡በኢየሩሳሌም፡ያለ፡የእግዚአብሔር፡ማደሪያ፡ቤተ፡መቅደስ፡ይሠሩ፡ጀመረ፡ከዚያም፡ቀን፡ጀምሮ፡እስከ፡ዛሬ፡ድረስ፡ይሠሩ፡ነበር፡ነገር፡ግን፡አልጨረሱም። ፳፤
አሁንም፡አቤቱ፡ንጉሥ፡በባቢሎን፡ያለ፡የንጉሡ፡የቂሮስ፡መንግሥት፡ወግ፡ታሪክ፡ ፳፩፤

የተጻፈባቸው ፡ መጻሕፍቶችን ፡ ገልጠህ ፡ መር
ምር ።
፳፩ በኢየሩሳሌም ፡ ያለ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡
ቤት ፡ መቅደስን ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ንጉሡ ፡ ቂሮስ ፡
እንደ ፡ ወደደላቸው ፡ ብታገኝ ፡ አቤቱ ፡ ንጉሥ ፡
አንተም ፡ ወደህላቸው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ስለዚህ ፡
ነገር ፡ ላክልን ።
፳፪ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ንጉሡ ፡ ዳርዮስ ፡ በባቢሎን ፡
ያሉ ፡ ወግ ፡ ታሪክ ፡ የተጻፈባቸው ፡ መጽሐፎ
ችን ፡ ይፈልጉ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፡ የሚዮን ፡ አው
ራጃ ፡ የሆነ ፡ የበረ ፡ ክፍል ፡ በሚሆን ፡ ወግ ፡
ታሪክ ፡ ጽፈው ፡ በኖሩበት ፡ ባንድ ፡ ቦታ ፡ በጠ
ኂስ ፡ በሚባል ፡ አገር ፡ ተገኘ ፡ የተገኘውም ፡
ደብዳቤ ፡ እንዲህ ፡ የሚል ፡ ነው ።
፳፫ ንጉሡ ፡ ቂሮስ ፡ በነገሠ ፡ በመጀመሪያው ፡
ዘመን ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ያለ ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡
በእሳት ፡ መሥዋዕት ፡ የሚሠዉበትን ፡ የእግዚ
አብሔር ፡ ማደሪያ ፡ ቤተ ፡ መቅደስን ፡ ይሠሩ ፡
ዘንድ ፡ አዘዘ ።
፳፬ አቆልቋዩ ፡ ስሳ ፡ ክንድ ፡ የሆነ ፡ ሥራውም ፡
በሦስት ፡ ወገን ፡ ማዕዘን ፡ ባለው ፡ ደንጊያ ፡
የሆነ ፡ ባንዲት ፡ ወገን ፡ የሚሆን ፡ ማገሩም ፡
ጽኑ ፡ በሚሆን ፡ ዋንዛ ፡ ዝግባ ፡ እንጨት ፡ የሆ
ነበት ፡ መቅደስን ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፡ ለጥ
ቃቅን ፡ ሥራ ፡ የሚሆነውንም ፡ ገንዘብ ፡ ከን
ጉሡ ፡ ከቂሮስ ፡ ዕቃ ፡ ቤት ፡ ይሰጧቸው ፡
ዘንድ ።
፳፭ ናቡከደነፆር ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ካለ ፡ ከቤተ ፡ መቅ
ደስ ፡ አውጥቶ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ የወሰደውን ፡
የብርና ፡ የወርቅ ፡ የሚሆን ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ማደሪያ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ንዋየ ፡ ቅድሳት ፡ በኢ
የሩሳሌም ፡ ወዳለ ፡ ቀድሞ ፡ ወደነበረበት ፡ ወደ
ዚያ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ይመልሱት ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ።
፳፮ የፈንቂስና ፡ የሶርያ ፡ አለቃ ፡ ሲሶኒስ ፡ እስተቦር ፡
ዘንስም ፡ ከነርሳቸው ፡ ጋራ ፡ ያሉ ፡ ባልንጀሮቻ
ቸውም ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ በፈንቂስና ፡ በሶርያ ፡
የተሾሙ ፡ እነዚያም ፡ ቦታቸውን ፡ ይተዉላ
ቸው ፡ ዘንድ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ ቤተ ፡
መቅደስን ፡ በቦታው ፡ ይሠሩት ፡ ዘንድ ፡ በይ
ሁዳ ፡ ላሉ ፡ ሽማግሎችና ፡ የይሁዳ ፡ አለቃ ፡
ዘሩባቤልም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ያሰናብቷቸው ፡
ዘንድ ፡ አዘዘ ።
፳፯ እኔም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ ቤተ ፡ መቅ
ደስን ፡ ሠርተው ፡ እስኪፈጽሙ ፡ ድረስ ፡ ከተ
ማረኩበት ፡ ከፋርስ ፡ ከባቢሎን ፡ የተመለሱ ፡
የአይሁድ ፡ ወገኖች ፡ ሁሉ ፡ አንድ ፡ ሁነው ፡
ተሰማርተው ፡ የእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ ቤተ ፡
መቅደስን ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ሥሩ ፡ ብዬ ፡ አዘዝ
ኋቸው ።
፳፰ የሶርያ ፡ ክፍል ፡ ከምትሆን ፡ ከቄሌክፋንቂስ ፡
የሚገባውን ፡ ግብር ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መሥ
ዋዕት ፡ የሚሆኑትን ፡ ፍየሎችን ፡ ላሞችን ፡
በጎችንም ፡ እንደ ፡ ሥርዓቱ ፡ ሰጥቻችሁ ፡ እን
ዚህን ፡ ሰዎች ፡ ደስ ፡ አሰኛቸው ፡ ንጉሡ ፡ ዘሩ
ባቤልንም ፡ ደስ ፡ አሰኙት ።
የሚያነዱት ፡ እንጨት ፡ ወይኑንና ፡ ጨዉን ፡ ፳፱
ዘይቱንም ፡ የሚገዙበትን ፡ ጥቃቅኑን ፡ ገንዘብ ፡
ሁሉ ፡ ክንድ ፡ ዓመት ፡ ወደ ፡ አንዱ ፡ ዓመት ፡
የሚያደርሳቸውን ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ያሉ ፡ ካህ
ናቱ ፡ ያዒችሁን ፡ ያህል ፡ ዘወትር ፡ ስጧቸው ፡
ግብሩንም ፡ ስትከራከሩ ፡ እነርሱ ፡ አምጡ ፡
እንዳይሉችሁ ፡ የሚበቃቸውን ፡ ስጧቸው ።
ስለ ፡ ንጉሡ ፡ ስለ ፡ ልጆቹም ፡ ገናና ፡ ለሆነ ፡ ለእ ፴
ግዚአብሔር ፡ ቍርባኑን ፡ ያቀርቡ ፡ ዘንድ ፡ በሕ
ይወትም ፡ እኑሯቸው ፡ ብለው ፡ ይለምኑላቸው ፡
ዘንድ ፡ ስጧቸው ።
በዚች ፡ ደብዳቤ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ አልሠራም ፡ ፴፩
ያለ ፡ አልሰጥምም ፡ ብሎ ፡ የተከራከራቸው ፡
ሰውም ፡ ቢኖር ፡ የራሱን ፡ እንጨት ፡ አምጥ
ተው ፡ በዚያ ፡ ይስቀሉት ፡ ገንዘቡንም ፡ ወር
ሰው ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ቤት ፡ ያግቡት ።
ስለዚህም ፡ ነገር ፡ በቤተ ፡ መቅደስ ፡ ስሙ ፡ የተ ፴፪
ጠራ ፡ እርሱ ፡ እግዚአብሔር ፡ አሕዛብን ፡ ሁሉ ፡
ያጥፋቸው ፡ የቤተ ፡ መቅደስን ፡ ሥራ ፡ ይከለክ
ሏቸው ፡ ዘንድ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ባለ ፡ በዚያ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ በቤተ ፡ መቅደስም ፡
ክፉ ፡ ሥራ ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ቃላቸውን ፡ ከፍ ፡
ከፍ ፡ የሚያደርጉ ፡ ነገሥታትንም ፡ ሁሉ ፡ እርሱ ፡
እግዚአብሔር ፡ ያጥፋቸው ።
እንዲህ ፡ አድርገው ፡ ተግተው ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ፴፫
እኔ ፡ ዳርዮስ ፡ አዘዝሁ ።

ምዕራፍ ፡ ፯ ።

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ የሶርያ ፡ ክፍል ፡ የምትሆን ፡ ፩
የቂሌ ፡ የፈንቂስም ፡ አለቃ ፡ ሲሳኒስ ፡ እስተረቡ
ዘኒስ ፡ ባልንጀሮቻቸውም ፡ ንጉሡ ፡ ዳርዮስ ፡ እን
ዳዘዘ ፡ ቤተ ፡ መቅደስን ፡ ይሠሩ ፡ ጀመሩ ።
እነርሱም ፡ ተግተው ፡ እያዘዙ ፡ ከአይሁድ ፡ ሽማ ፪
ግሎች ፡ ጋራ ፡ ተቀመጡ ።
ቤተ ፡ መቅደሱም ፡ ፈጥኖ ፡ ተሠራ ፡ መምህራን ፡ ፫
የሚሆኑ ፡ ሐጌና ፡ ዘካርያስ ፡ ትንቢት ፡ እየተና
ገሩላቸው ፡ የተለየ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሠሩ ።
ዳርዮስና ፡ ቂሮስ ፡ የፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ አርጤክ ፬
ስስ ፡ ባወቁ ፡ ገንዘብ ፡ በእስራኤል ፡ ፈጣሪ ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ ቤተ ፡ መቅደስን ፡ ሠር
ተው ፡ ጨረሱ ፡ የፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ ዳርዮስ ፡ በነ
ገሠ ፡ በስድስተኛው ፡ ዘመን ፡ ተጨረሰ ።
ጨረቃ ፡ ሕፀፅ ፡ ባደረገበት ፡ በስምንተኛው ፡ ፭
ቀን ፡ በመጋቢት ፡ ወር ፡ ዳርዮስ ፡ በነገሠ ፡ በስ
ድስተኛው ፡ ዘመን ፡ የቤተ ፡ መቅደስ ፡ ሥራ ፡
አለቀ ።
የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ካህናቱም ፡ ሌዋውያንም ፡ ፮
ከተማረኩበት ፡ የተመለሱት ፡ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡
በሙሴ ፡ መጣፍ ፡ እንደ ፡ ተጣፈ ፡ ሥርዓቱን ፡
አደረጉ ።
የእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ መታ ፯
ደሻውን ፡ አደረጉ ፡ መቶ ፡ ላሞችን ፡ ሁለት ፡
መቶ ፡ ፍየሎችን ፡ አራት ፡ መቶ ፡ በጎችን ፡ አረዱ ።

፯ ፤ በሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ነገደ ፡ እሥራኤል ፡ ሹማምንት ፡
ቊጥር ፡ ስለ ፡ እስራኤል ፡ ኃጢአት ፡ ሁሉ ፡
አሥራ ፡ ሁለት ፡ ሙክቶችን ፡ ሠዉ ።
፰ ፤ በሙሴ ፡ መጣፍ ፡ በአሪቱ ፡ እንደ ፡ ተጣፈ ፡
እንደ ፡ ሥርዓታቸው ፡ የቤተ ፡ እግዚአብሔር ፡
ሥራ ፡ ለመሥራት ፡ በየወገናቸውም ፡ ልብሰ ፡
ተክህኖውን ፡ ለብሰው ፡ ክህናቱና ፡ ሌዋውያን ፡
ቆሙ ፡ የቤተ ፡ መቅደስን ፡ ደጃፍ ፡ የሚዘጉ ፡ በረ
ኞችም ፡ በየደጃፋቸው ፡ ቆሙ ።
፲ ፤ ክህናቱ ፡ ሌዋውያንም ፡ ሁሉ ፡ አንድ ፡ ሁነው ፡
ሰውነታቸውን ፡ ንጹሕ ፡ አድርገዋልና ፡ ከተማ
ረኩበት ፡ የተመለሱ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡
መጀመሪያ ፡ ወር ፡ በባተ ፡ በሥራ ፡ አራተኛው ፡
ቀን ፡ በዓል ፡ አደረጉ ።
፲፩ ፤ ሌዋውያን ፡ ሁሉ ፡ ሰውነታቸውን ፡ አንጽተው ፡
ነበርና ፡ ከተማረኩት ፡ የተመለሱት ፡ ልጆቻ
ቸው ፡ ግን ፡ ሰውነታቸውን ፡ ከኃጢአት ፡ አላ
ነጹም ።
፲፪ ፤ ለተማረኩ ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ለወንድሞ
ቻቸው ፡ ለካህናት ፡ ለጋቸውን ፡ ሠዉ ።
፲፫ ፤ ተማርከው ፡ የነበሩ ፡ በሕግ ፡ በአምልኮት ፡ እግ
ዚአብሔርን ፡ ይሹት ፡ ዘንድ ፡ በገር ፡ ካሉ ፡ ከአ
ሕዛብ ፡ በኃጢአታቸው ፡ የተለዩ ፡ የእስራኤል ፡
ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ተረፈ ፡ መሥዋዕቱን ፡ በሉ ።
፲፬ ፤ በእግዚአብሔር ፡ ደስ ፡ ብሏቸው ፡ ቂጣውን ፡
እየበሉ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ በዓል ፡ አደረጉ ።
፲፭ ፤ የፋርሱ ፡ ንጉሥ ፡ የዳርዮስን ፡ ልቡና ፡ ወደ ፡
በጎነት ፡ መልሶ ፡ የእስራኤል ፡ ፈጣሪ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ የሚመሰገንበትን ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡
ለመሥራት ፡ እጃቸውን ፡ አጽንቶላቸዋልና ፡
በዓል ፡ አደረጉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ ፤ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ የፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ አርጤክ
ስስ ፡ በነገሠ ፡ ጊዜ ፡ የአዛርያስ ፡ ልጅ ፡ ዕዝራ ፡
መጣ ፡ አዛርያስን ፡ የኤክርዩ ፡ ልጅ ፡ አለው ፡
ኤክርዩንም ፡ የኬልቅዩ ፡ ልጅ ፡ አለው ፡ ኬል
ቅዩንም ፡ የሴሎም ፡ ልጅ ፡ አለው ።
፪ ፤ ሴሎምን ፡ የሴድሎቱ ፡ ልጅ ፡ አለው ፡ ሴድሎ
ቱን ፡ የአኪጦብ ፡ ልጅ ፡ አለው ፡ አኪጦብን ፡
የአመርትዩ ፡ ልጅ ፡ አለው ፡ አመርትዩን ፡ የአ
ዝያን ፡ ልጅ ፡ አለው ፡ አዝያንን ፡ የበቃ ፡ ልጅ ፡
አለው ፡ በቃን ፡ የአቤሲ ፡ ልጅ ፡ አለው ፡ አቤ
ሲን ፡ የፊንሐስ ፡ ልጅ ፡ አለው ፡ ፊንሐስን ፡
የአልዓዛር ፡ ልጅ ፡ አለው ፡ አልዓዛር ፡ የመጀ
መሪያው ፡ ካህን ፡ የአሮን ፡ ልጅ ፡ ነው ።
፫ ፤ ይህም ፡ ዕዝራ ፡ ከባቢሎን ፡ መጣ ፡ የእስራ
ኤል ፡ ፈጣሪ ፡ ለሙሴ ፡ ጽፎ ፡ የሰጠውን ፡ ኦሪ
ትንም ፡ ሁሉ ፡ ያውቅ ፡ ነበረ ፡ መጽሐፉንም ፡
እርሱ ፡ ጻፈ ።
፬ ፤ በፊቱ ፡ ባለሟልነትን ፡ አግኝቷልና ፡ በሥራ
ውም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ይሾሙታልና ፡ ንጉሡም ፡
ሹመት ፡ ሰጠው ።
፭ ፤ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ክህናቱ ፡ ሌዋውያንም ፡
ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወጡ ፡ ግናያቱን ፡ የሚያ
ደርሱ ፡ ክህናት ፡ የክህናቱም ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡
ኢየሩሳሌም ፡ ወጡ ።
አርጤክስስ ፡ በነገሠ ፡ በሰባተኛው ፡ ዓመት ፡ ፮ ፤
በምስተኛው ፡ ወር ፡ በወሩ ፡ መባቻ ፡ ከባቢሎን ፡
ወጡ ።
እግዚአብሔር ፡ መንገዳቸውን ፡ እንዳቀናላቸው ፡ ፯ ፤
መጠን ፡ በመጀመሪያው ፡ ወር ፡ መባቻ ፡ ወደ ፡
ኢየሩሳሌም ፡ ደረሱ ።
ዕዝራ ፡ ግን ፡ ብዙ ፡ ትምህርት ፡ የተማረ ፡ ነበረ ፡ ፰ ፤
ከእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ በእስራኤል ፡ ከታዘ
ዘው ፡ ትእዛዝ ፡ ሁሉ ፡ ከተሠራውም ፡ ሥርዓት ፡
ከሚፈርዱትም ፡ ፍርድ ፡ ወጥቶ ፡ በኃጢአት ፡
አይስትም ፡ ነበር ።
ንጉሡ ፡ አርጤክስስም ፡ አገልጋይ ፡ ወደ ፡ ሆነ ፡ ፱ ፤
የእግዚአብሔርንም ፡ ሕግ ፡ ወደሚጽፍ ፡ ወደ ፡
ዕዝራ ፡ ላከ ።
ከንጉሡ ፡ አርጤክስስ ፡ አገልጋይ ፡ ወደ ፡ ሆነ ፡ ፲ ፤
የእግዚአብሔርንም ፡ ሕግ ፡ ወደሚጽፍ ፡ ወደ ፡
ዕዝራ ፡ የተላከ ፡ ደብዳቤም ፡ እንዲህ ፡ የሚል ፡
ነው ።
እኔ ፡ ሰውን ፡ በመውደድ ፡ አስቤ ፡ ከአይሁድ ፡ ፲፩ ፤
ወገን ፡ ከካህናት ፡ በምገዛው ፡ አገር ፡ ካሉ ፡ ከሌ
ዋውያንም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፡
ከወደዱ ፡ የሚወዱትን ፡ ሁሉ ፡ ይሂዱ ፡ ብዬ ፡
አዝዣለሁና ፡ አንተን ፡ ደስ ፡ ይበልህ ፡ የምትል ፡
ናት ።
ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፡ የሚወዱ ፡ ፲፪ ፤
ሁሉ ፡ ይሁዳንና ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ አይተው ፡
ከናንተ ፡ ጋራ ፡ በሥራ ፡ አንድ ፡ ይሁኑ ፡ የም
ትል ፡ ናት ።
እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘው ፡ ሥርዓት ፡ ሂደው ፡ ፲፫ ፤
በዓል ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ሰባቱ ፡ ባለሟሎቼና ፡
እኔ ፡ አማካሪዎቼም ፡ እንዲህ ፡ አዘናልና ።
ቍርባኑን ፡ ባለሟሎቼንና ፡ እኔ ፡ የተሳለውን ፡ ፲፬ ፤
ስእለት ፡ በባቢሎን ፡ የተገኘውን ፡ ብርና ፡ ወር
ቁን ፡ ሁሉ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ባለው ፡ ቤተ ፡ መቅ
ደስ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ያቀርቡ ፡ ዘንድ ፡ አዘ
ናልና ።
ሕዝቡ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ባለ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፲፭ ፤
ማደሪያ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ከሚያገቡት ፡ ስእ
ለት ፡ ጋራ ፡ ወርቅና ፡ ብሩን ፡ ፍሪዳውንም ፡ ፍየ
ሉን ፡ በጉንም ፡ ይሰብስቡ ፡ አለ ።
እንደ ፡ ሥርዓታቸው ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ባለው ፡ ፲፮ ፤
በእግዚአብሔር ፡ መሠዊያ ፡ መሥዋዕት ፡ በሚ
ሠዉ ፡ ገንዘብ ፡ ፈቃዳቸውን ፡ የሚፈጽሙበ
ትን ፡ ሁሉ ፡ ይሰብስቡ ፡ አለ ።
ከባልንጀራህ ፡ ጋራ ፡ ታደርገው ፡ ዘንድ ፡ የምት ፲፯ ፤
ወደውን ፡ ሁሉ ፡ ፈጣሪህ ፡ እንደሚወደው ፡
አድርገህ ፡ በዚህ ፡ በሰደድሁልህ ፡ ወርቅና ፡
ብር ፡ ሥራ ።
ንዋየ ፡ ቅድሳቱን ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ያለ ፡ ፈጣ ፲፰ ፤
ሪህ ፡ የሚመሰገንበት ፡ የቤተ ፡ መቅደስ ፡ ግዳጅ ፡
የሚሆነውን ።

፲፱፡ ፈጣሪያችሁ፡የሚመሰገንበት፡የምስጋናውን፡
መቃሰቢያ፡የምትሹት፡ሌላም፡ነገር፡ቢኖር፡
ከንጉሡ፡ዕቃ፡ቤት፡እስጣለሁ።
፳፡ አገልጋይ፡የሆነ፡የገናና፡የእግዚአብሔርንም፡
ሕግ፡ የሚጽፍ፡ ዕዝራ፡ ይሰጡት፡ ዘንድ፡
ስጡኝ፡ ያላችሁን፡ በሶርያና፡ በፊንቂስ፡
ከለው፡ ዕቃ፡ ቤት፡ አውጥታችሁ፡ ስጡት፡
እምቢ፡ አትበሉ፡ ብዬ፡ እኔ፡ አርጤክስስ፡ አዘ
ዝሁ።
፳፩፡ መቶ፡ መክሊት፡ ብር፡ ዳግመኛም፡ ቁሮስ፡
በሚባል፡መቶ፡መስፈሪያ፡ስንዴን።
፳፪፡ እባል፡በሚባል፡መስፈሪያ፡መቶ፡መስፈሪያ፡
ወይንም፡ስጡ፡ብዬ፡አዘዝሁ።
፳፫፡ በንጉሥ፡ መንግሥት፡ በልጆቹም፡ መከራ፡
እንዳይመጣ፡በገናና፡በእግዚአብሔር፡ሕግ፡
ጸንተው፡መሥዋዕቱን፡ይሠዉ፡ዘንድ፡አዘ
ዝኩ።
፳፬፡ ከካህናት፡ከሌዋውያንም፡ግናያቱን፡ከሚያደ
ርሱ፡ ከካህናት፡ በሩንም፡ ከሚዘጉ፡ ከካህና
ቱም፡ልጆች።
፳፭፡ ቤተ፡ መቅደስን፡ ከሚያገለግልም፡ ሁሉ፡
ምንም፡ ምን፡ ግብር፡ አትቀበሉ፡ በምንም፡
በምን፡አትግዟቸው።
፳፮፡ ዕዝራ፡አንተም፡እግዚአብሔር፡በገለጠልህ፡
ጥበብ፡የፈጣሪህን፡ሕግ፡ከሚያውቁ፡ወገን፡
የሚሆኑ፡ፊንቂስንና፡ሶርያን፡የሚገዙ፡መኳ
ንንቱን፡ መሳፍንቱን፡ ሹም፡ ሕገ፡ እግዚአብ
ሔርን፡ የማያውቁትንም፡ አስተምራቸው።
፳፯፡ የፈጣሪህን፡ሕግ፡የንጉሡንም፡ትእዛዝ፡እምቢ፡
የሚለውን፡ ሁሉ፡ ቸል፡ አትበሉ፡ ቅጡት፡
ሞት፡የሚገባውን፡ግደሉት፡ግርፋት፡የሚገ
ባውን፡ግረፉት፡መገዛት፡የሚገባውን፡ግዙት፡
መወረስ፡ የሚገባውን፡ ውረሱት፡ ሁሉንም፡
በየኃጢአቱ፡ቅጡት።
፳፰፡ በኢየሩሳሌም፡ያለ፡የእግዚአብሔር፡ማደሪያ፡
ቤተ፡ መቅደስን፡ አክብር፡ ዘንድ፡ እንዲህ፡
ያለውን፡ዕውቀት፡ለኔ፡ለንጉሥ፡በልቤ፡ያሳ
ደረ፡እግዚአብሔር፡ይክበር፡ይመስገን፡አለ።
፳፱፡ ከነገሥታቱ፡ ከወዳጆቹም፡ ሁሉ፡ ከመኳንን
ቱም፡ ሁሉ፡ እኔን፡ አክብሮኛልና፡ ይክበር፡
ይመስገን።
፴፡ አርጤክስስ፡እንዲህ፡ብሎ፡ከተናገረ፡በኋላ፡
ዕዝራ፡በፈጣሪዬ፡በእግዚአብሔር፡ረድኤት፡
ታመንሁ።
፴፩፡ በሚያ፡በሥራ፡ከባልንጀሮቻቸው፡የተከከሉ፡
ከእስራኤል፡ወገን፡ከኔ፡ጋራ፡ወደ፡ኢየሩሳ
ሌም፡ የመጡትን፡ በሥራም፡ ከባልንጀሮቻ
ቸው፡የተከከሉትን፡ሰዎች፡አመጣሁ፡ በየገ
ራቸው፡በየአውራጃቸውም፡አገዛዝ፡ጸንተው፡
የሚኖሩ፡ንጉሡ፡አርጤክስስ፡በነገሥ፡ጊዜ፡
ከኔ፡ጋራ፡ከባቢሎን፡የወጡን፡አመጣሁ።
፴፪፡ ከፎሮስም፡ልጆች፡ጣዕሞስን፡ከኢዮጥማሩም፡
ልጆች፡ጋሚሉስን።
፴፫፡ ከዳዊትም፡ልጆች፡ፋሬስን፡ዘከርያስን፡አመ
ጣሁ፡ ከርሱም፡ ጋራ፡ መቶ፡ አምሳ፡ ሰዎች፡
ተቈጥረው፡መጡ።
ከፎአት፡ሞዓብም፡ ልጆች፡ ቢሕያስን፡ ዜር ፴፬፡
ዩንም፡አመጣሁ፡ከርሱም፡ጋራ፡ሁለት፡መቶ፡
ሰዎች፡ተቈጠሩ።
ከዘቶይስም፡ልጆች፡ኢያኬንያስን፡ኢየሐቴ ፴፭፡
ሉን፡አመጣሁ፡ከርሱም፡ጋራ፡ሁለት፡መቶ፡
ሰዎች፡ተቈጠሩ፡ከአዲኑቢኑም፡ልጆች፡ዘዮ
ናቱን፡ አመጣሁ፡ ከርሱም፡ ጋራ፡ ሁለት፡
መቶ፡አምሳ፡ሰዎች፡ተቈጠሩ።
ከአሚስያም፡ልጆች፡ዘጎቶልዩን፡አመጣሁ፡ ፴፮፡
ከርሱም፡ጋራ፡ሰባ፡ሰዎች፡ተቈጠሩ።
ከከፎጡር፡ልጆች፡ዘከርያስን፡ዘሚከኤሉን፡ ፴፯፡
አመጣሁ፡ከርሱም፡ጋራ፡ ሰባ፡ ሰዎች፡ ተቈ
ጠሩ።
ከኢዮአብም፡ ልጆች፡ ዘበዱያስን፡ ዘኢየዚ ፴፰፡
ሉን፡አመጣሁ፡ከርሱም፡ጋራ፡ሁለት፡መቶ፡
አሥራ፡ሁለት፡ሰዎች፡ተቆጠሩ።
ከባኒ፡ ልጆችም፡ እስሊሞትን፡ ዘኢዮስፌ ፴፱፡
ዩን፡አመጣሁ፡ከርሱም፡ጋራ፡መቶ፡ስድሳ፡
ሰዎች፡ተቈጠሩ።
ከቤኤርም፡ልጆች፡ዘከርያስን፡ዘቤቢን፡አመ ፵፡
ጣሁ፡ከርሱም፡ጋራ፡ኻያ፡ስምንት፡ሰዎች፡
ተቈጠሩ።
ከአስጣያትም፡ ልጆች፡ ዮሐንስን፡ ዘአቃጣ ፵፩፡
ንን፡አመጣሁ፡ከርሱም፡ጋራ፡መቶ፡ሃምሳ፡
ሰዎች፡ተቆጠሩ።
ከአዳንያም፡ ልጆች፡ የቀሩትን፡ ሁሉ፡ አመ ፵፪፡
ጣሁ፡ስማቸው፡ ይህ፡ ነው፡ ኤሊ፡ ፋሌ፡ ዘጌ
ሁአል፡ ሰሚያስ፡ ይባላል፡ ከርሱም፡ ጋራ፡
መቶ፡ሰዎች፡ተቆጠሩ፡ከቤኑስም፡ልጆች፡
እስጣስቆሩን፡አመጣሁ፡ከርሱም፡ጋራ፡ሰባ፡
ሰዎች፡ተቈጠሩ።
ይብሉ፡ ወደሚባል፡ ወንዝ፡ ወሰድኋቸው፡ ፵፫፡
በዚያ፡ሦስት፡ቀን፡አደርን።
የቈጣጠርኋቸው፡ከነርሱ፡ካህናትን፡ሌዋው ፵፬፡
ያንን፡አላገኘንም።
ወደ፡አልዓዛርም፡ልኬ፡ከኔ፡ጋራ፡የሚሄዱ፡ ፵፭፡
መሰስመንን፡ አንግግንን፡ ምያሳን፡ ኢዮብባ
ንን፡ዘናታንን፡ዘአርጠንን፡ዘዘከርያንም፡ተቀ
በልሁ፡ከዚህም፡ጋራ፡ከሹሞቻቸውም፡ከዋ
ቆቻቸውም፡ ወገን፡ የሚሆኑ፡ ሰዎችን፡ ተቀ
ብዬ።
ዕቃ፡ ቤት፡ ጠባቂ፡ ወደሚሆን፡ ወደ፡ ያድ ፵፮፡
ዮን፡ይሄዱ፡ዘንድ፡ሂዱ፡አልኋቸው።
የእግዚአብሔርን፡ማደሪያ፡ቤተ፡መቅደስን፡ ፵፯፡
ለሚያገለግሉ፡ ለካህናት፡ አለቆች፡ ሰዎችን፡
ይሰዱላቸው፡ ዘንድ፡ ለያድዮን፡ ለወንድሞ
ቹም፡በዚያም፡አገር፡ለሚኖሩ፡ሰዎች፡ ንገሯ
ቸው፡ብዬ፡አዘዝኋቸው።
ሌዋዊ፡ እስራኤላዊ፡ ከሚሆን፡ ከመሐሊ፡ ፵፰፡
ልጆች፡አኪብያን፡ልጆቹንም፡አሥሩን፡ወን
ድሞቹንም፡ይሰዱ፡ዘንድ፡አዘዝሁ።
ከከአኑ፡ልጆች፡ከልጅ፡ልጆቻቸውም፡ኻያ፡ ፵፱፡

ሰዎች ፡ ጨምረው ፡ ይሰዱ ፡ ዘንድ ።
፶፤ ዳዊት ፡ የሠራቸው ፡ የካህናት ፡ ልጆች ፡ ታላላቆ
ችም ፡ ሌዋውያን ፡ ለሚሠሩት ፡ ሥራ ፡ የተጨ
መሩት ፡ የካህናት ፡ ልጆች ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ኻያ ፡
ናቸው ፡ የሁሉም ፡ ስማቸው ፡ ተጻፈ ።
፶፩፤ በፊጣሪያችን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ከልጆ
ቻችን ፡ ጋራ ፡ በዚያ ፡ እንጾም ፡ ዘንድ ፡ ለልጆ
ቻችንም ፡ ለከብቶቻችንም ፡ ይቅርታን ፡ እንለ
ምን ፡ ዘንድ ፡ ተሳልን ።
፶፪፤ አገራችንን ፡ የሚያጸኑ ፡ ከጠላቶቻችን ፡ ጋራ ፡
የሚመክቱ ፡ የሚወራወሩ ፡ ፈረሰኞች ፡ እግ
ረኞችንም ፡ እልክ ፡ ዘንድ ፡ ታዝዥለሁና ፡ እን
ጾም ፡ ዘንድ ፡ ተሳልን ።
፶፫፤ ሥራውን ፡ ሁሉ ፡ ያቀናላቸው ፡ ዘንድ ፡ በሕግ ፡
በአምልኮት ፡ ከሚፈልጉት ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ የጌ
ታችን ፡ ከሀሊነት ፡ እንዳለ ፡ ንጉሡን ፡ ለምነዋ
ልና ።
፶፬፤ ስለዚህ ፡ ሁሉ ፡ ነገር ፡ ዳግመኛ ፡ ወደ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ለመነ ፡ እርሱም ፡ ይቅር ፡ አለን ።
፶፭፤ በሕዝብ ፡ ላይ ፡ በካህናቱም ፡ ላይ ፡ የተሾሙ ፡
አሥራ ፡ ሁለቱን ፡ ሹማምንት ፡ ለየኋቸው ፡ ከወ
ንድሞቻቸው ፡ ወገን ፡ ከሚሆኑ ፡ ከሥሩ ፡ ሰዎ
ችም ፡ ጋራ ፡ አሲሚያንና ፡ ኤሴሬያን ፡ አሉ ።
፶፮፤ የእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ ቤተ ፡ መቅደስን ፡
የሚያገለግሉበት ፡ ንዋየ ፡ ቅድሳቱን ፡ ወርቁንና ፡
ብሩን ፡ ንጉሥ ፡ የሰጠንን ፡ መኳንንቱና ፡ አማካ
ሪዎቹ ፡ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ የሰጡንን ፡ መዝኜ ፡
ሰጠኋቸው ።
፶፯፤ ስድስት ፡ መቶ ፡ አምሳ ፡ መክሊት ፡ ብርም ።
፶፰፤ መቶ ፡ መክሊት ፡ የተሠራ ፡ የብር ፡ ዕቃ ፡ መቶ ፡
መክሊት ፡ ወርቁንም ፡ የተሠራ ፡ ኻያ ፡ የወርቅ ፡
ዕቃም ፡ ያማረ ፡ እንደ ፡ ወርቅ ፡ የጠራ ፡ አሥር ፡
የብርት ፡ ዕቃም ፡ መዝኜ ፡ ሰጠኋቸው ።
፶፱፤ እናንተም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ተለዩ ፡ የብር ፡ የወ
ርቅ ፡ የሆነ ፡ ንዋየ ፡ ቅድሳቱንም ፡ ለዩ ፡ ለአባቶ
ቻችን ፡ ፈጣሪ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የተሳላችሁ
ትን ፡ ስእለቱንም ፡ ስጡ ።
፷፤ ለመሳፍንቱ ፡ ለመኳንንቱ ፡ ለሌዋውያንና ፡ ለካ
ህናቱ ፡ ወገኖች ፡ እስክትሰጧቸው ፡ ድረስ ፡ ተግ
ታችሁ ፡ ተጠበቁ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ በፊጣሪያ
ችን ፡ ማደሪያ ፡ በቤተ ፡ መቅደስ ፡ ለእስራኤል ፡
ለአለቆቻቸው ፡ ሹማምንት ፡ እስክትሰጡ ፡
ድረስ ፡ ተግታችሁ ፡ ጠብቁ ፡ አልኋቸው ።
፷፩፤ ካህናቱ ፡ ሌዋውያንም ፡ የተቀበሉትን ፡ ወርቁን ፡
ብሩን ፡ የኢየሩሳሌምንም ፡ ንዋየ ፡ ቅድሳቱን ፡
እግዚአብሔር ፡ ወደሚመሰገንበት ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡
መቅደስ ፡ አገቡ ።
፷፪፤ የመጀመሪያው ፡ ወር ፡ ሚያዝያ ፡ በባተ ፡ በሥራ ፡
ሁለተኛው ፡ ቀን ፡ ቴራ ፡ ከሚባል ፡ ከዚያ ፡ አገር ፡
ተነሥተው ፡ ከጠላቶቻችን ፡ ሁሉ ፡ እጅ ፡ ያዳ
ነን ፡ ጽንዕት ፡ በምትሆን ፡ ከኛ ፡ ጋራ ፡ ባለች ፡
በፊጣሪያችን ፡ ሥልጣን ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ደረሱ ።
፷፫፤ ኢየሩሳሌምም ፡ በደረሱ ፡ በሦስተኛው ፡ ቀን ፡
ወርቁን ፡ ብሩን ፡ መዝነው ፡ በየወገኑ ፡ ቈጥረው ፡
ቤተ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለሚጠብቅ ፡ መርሞቴ
ዶራ ፡ ለሚባል ፡ ካህን ፡ ሰጡት ።
ልኩ ፡ ሁሉ ፡ ሚዛኑም ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ ተጻፈ ። ፷፬፤
ከርሱ ፡ ጋራ ፡ የፊንሐስ ፡ ልጅ ፡ አልዓዛር ፡ ነበር ፡ ፷፭፤
ከነርሳቸውም ፡ ጋራ ፡ ሌዋውያን ፡ የሚሆኑ ፡
የብኑ ፡ ልጅ ፡ ሞኢተስና ፡ የኢዮስያስ ፡ ልጅ ፡
ዮስዝዲስ ፡ ነበሩ ።
ከተማረኩበት ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ የተመለሱ ፷፮፤
ትም ፡ ለእስራኤል ፡ ፈጣሪ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
መሥዋዕት ፡ ሠዉ ።
አሥራ ፡ ሁለት ፡ ላሞችን ፡ ዘጠና ፡ ስድስት ፡ ፷፯፤
በጎችን ፡ ስለድኅነትም ፡ ሰባ ፡ ስድስት ፡ ሙክ
ቶችን ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ በግ ፡ ጠቦቶችን ፡ ይህ
ንን ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሠዉ ።
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በንጉሡ ፡ ዕቃ ፡ ቤት ፡ ለተሾሙ ፡ ፷፰፤
በሶርያ ፡ በፊንቂስ ፡ ለተሾሙ ፡ ሹማምንቶችም ፡
ከንጉሡ ፡ የመጣውን ፡ ደብዳቤ ፡ ሰጧቸው ፡
ሕዝቡንም ፡ አከበሩዋቸው ፡ የእግዚአብሔር ፡
ማደሪያ ፡ ቤተ ፡ መቅደስንም ፡ ሠሩላቸው ።
ሹማምቱም ፡ ወጥተው ፡ የሠሩትን ፡ ነገሩኝ ። ፷፱፤
የእስራኤል ፡ ወገኖች ፡ መኳንንቶቻቸውም ፡ ፸፤
ቢሆኑ ፡ ካህኖቻቸውም ፡ ሌዋውያንም ፡ ቢሆኑ ፡
በኢየሩሳሌም ፡ ያሉ ፡ ሌሎች ፡ አሕዛብ ፡ ከሚ
ሠሩት ፡ ኃጢአት ፡ አልተለዩም ፡ አሉኝ ፡ አሕ
ዛብም ፡ የተባሉ ፡ ከናኔዎን ፡ ፌርዜዎን ፡ ኬጤ
ዎንም ፡ ኢያቡሴዎን ፡ ሞዓቢጦን ፡ ግብጽ ፡ ኤዶ
ሚዎን ፡ ናቸው ።
የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ አገቡ ፡ የከበሩ ፡ ዘር ፡ ፸፩፤
የሆኑ ፡ እስራኤል ፡ እነርሳቸውም ፡ ልጆቻቸ
ውም ፡ በገር ፡ ካሉ ፡ ልዩ ፡ ከሆኑ ፡ ከአሕዛብ ፡
ጋራ ፡ በግብር ፡ አንድ ፡ ሆኑ ፡ ሹማምንቶቻ
ቸው ፡ መኳንንቶቻቸውም ፡ ከቀድሞ ፡ ግብራ
ቸው ፡ ወጥተው ፡ በዚች ፡ ኃጢአት ፡ አንድ ፡
ሆኑ ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ይህንን ፡ በሰማሁ ፡ ጊዜ ፡ ልብ ፸፪፤
ሴን ፡ ልብሰ ፡ ተክህኖዬንም ፡ ቀደድሁ ፡ የራ
ሴን ፡ ጠጉር ፡ ጢሜንም ፡ ነጨሁ ፡ ተክዤ ፡
አዝኜም ፡ ተቀመጥሁ ።
እኔ ፡ በዚች ፡ ኃጢአት ፡ ያዘንሁ ፡ የተከዝሁ ፡ ፸፫፤
ሁኜ ፡ ተቀምጬ ፡ ሳለሁ ፡ የእስራኤል ፡ ፈጣሪ ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ የሚፈሩ ፡ ሁሉ ፡
ወደ ፡ እኔ ፡ ተሰበሰቡ ።
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ የሠርኩን ፡ መሥዋዕት ፡ በሚ ፸፬፤
ያቀርቡበት ፡ ጊዜ ፡ ተረፈ ፡ መሥዋዕቱን ፡ ስለ ፡
በላ ፡ ልብሴን ፡ የክህነት ፡ ልብሴንም ፡ ቀድጄ ፡
ከጉልበቴም ፡ ተንበርክኬ ፡ እደ ፡ ልቡናዬንም ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረግሁ ።
አቤቱ ፡ አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ ከገጸ ፡ መዓትህ ፡ የተ ፸፭፤
ነሣ ፡ ፊርቼ ፡ ንስሐ ፡ አገባለሁ ።
ኃጢአታችን ፡ በዝታለችና ፡ ከራሳችንም ፡ ፸፮፤
ጠጉር ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብሏልና ።
ከአባቶቻችን ፡ ዘመን ፡ ጀምሮ ፡ የእግዚአብሔ ፸፯፤
ርን ፡ ሕግ ፡ ባለማወቃቸውም ፡ እስከ ፡ ሰማይ ፡
ደርሷልና ፡ እስከ ፡ ዛሬም ፡ ድረስ ፡ በጽኑ ፡ ኃጢ

አት ፡ ተይዘን ፡ ኖረናልና ።
፸፯፤ በኛ ፡ ኃጢአት ፡ በበዩቻችንም ፡ ኃጢአት ፡ የፋ
ርስ ፡ የባቢሎን ፡ ነገሥታት ፡ ከወንድሞቻችን ፡
ከጌቶቻችን ፡ ከካህኖቻችንም ፡ ጋራ ፡ በጦራ
ቸው ፡ ማርከው ፡ ወሰዱን ፡ እስከ ፡ ዛሬም ፡ ድረስ ፡
በመከራው ፡ አፈርን ።
፸፰፤ አሁን ፡ ግን ፡ በዚህች ፡ በከበረች ፡ በታ ፡ ልጅ ፡
የልጅ ፡ ልጅ ፡ የተወልን ፡ የእግዚአብሔር ፡
ቸርነቱ ፡ ፈጽማ ፡ ተደረገችልን ።
፹፤ እርሱ ፡ ፈጣሪያችን ፡ በማደሪያው ፡ ቤተ ፡ መቅ
ደስ ፡ ብርሃን ፡ ረድኤቱን ፡ ገለጠልን ፡ ተገዥዎ
ችም ፡ በሆንን ፡ ጊዜ ፡ ምግባችንን ፡ ሰጥቶን ፡
ነበር ።
፹፩፤ በተገዛንም ፡ ጊዜ ፡ ፈጣሪያችን ፡ በረድኤት ፡
አልተለየንም ፡ ምግባችንን ፡ ይሰጠን ፡ ዘንድ ፡
ጽዮንንም ፡ ፍራሿን ፡ ሠርተው ፡ ቤተ ፡ መቅደ
ሳችንን ፡ ያከብሩ ፡ ዘንድ ።
፹፪፤ በኢየሩሳሌምና ፡ በይሁዳ ፡ የሥራ ፡ ረዳትን ፡
ይሰጡን ፡ ዘንድ ፡ በፋርስ ፡ ነገሥታትም ፡ ፊት ፡
ባለሟልነትን ፡ ሰጠን ።
፹፫፤ አቤቱ ፡ አሁንስ ፡ ይህ ፡ መከራው ፡ በኛ ፡ ላይ ፡
ሳለ ፡ ምን ፡ እንናገራለን ፡ በባሮችህ ፡ በነቢያ
ትም ፡ ቃል ፡ ያዘዝኻቸውን ፡ ትእዛዝህን ፡ አፈ
ረሱ ።
፹፬፤ ምድርን ፡ ትወርሷት ፡ ዘንድ ፡ ወደርሷ ፡ ትገቧታ
ላችሁ ፡ ያልኻቸው ፡ ያች ፡ አገር ፡ በገር ፡ በሉ ፡
በአሕዛብ ፡ ኃጢአት ፡ የተደፈነች ፡ ናት ፡ ኃጢ
አታቸውንም ፡ መሏት ።
፹፭፤ ሴቶች ፡ ልጆቻችሁንም ፡ ለወንዶች ፡ ልጆቻ
ቸው ፡ አታጋቡ ።
፹፮፤ ድል ፡ ትነሷቸው ፡ ዘንድ ፡ የኢየሩሳሌምንም ፡
ድልቧን ፡ ትበሉ ፡ ዘንድ ፡ በዘመናችሁ ፡ ሁሉ ፡
ከነርሱ ፡ ጋራ ፡ አንድነት ፡ አትሁኑ ፡ ያልሃቸው ፡
ለልጆቻችሁም ፡ አገሪቱን ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ታወ
ርሷቸዋላችሁ ፡ ያልሃቸው ፡ አሕዛብ ፡ ኃጢአታ
ቸውን ፡ መሏት ።
፹፯፤ ይችም ፡ መከራ ፡ ሁሉ ፡ ያገኘችን ፡ ስለሥራችን ፡
ክፋት ፡ ስለኃጢአታችንም ፡ ብዛት ፡ ነው ።
፹፰፤ አቤቱ ፡ ጌታችን ፡ አንተ ፡ ግን ፡ ኃጢአታችንን ፡
ታግሠህ ፡ በምንመለስም ፡ ገንዘብ ፡ ልጅ ፡
ሰጠኸን ፡ ዳግመኛ ፡ ግን ፡ ሕግህን ፡ አፍርሰን ፡
በኃጢአታቸው ፡ በአገር ፡ ካሉ ፡ አሕዛብ ፡ ጋራ ፡
አንድ ፡ እንሆናለን ።
፹፱፤ ብትቈጣንስ ፡ ልጅ ፡ የልጅ ፡ ልጅ ፡ ስማችንንም ፡
እስከማጥፋት ፡ ደርሰህ ፡ ፈጽመህ ፡ ባጠፋኸን ፡
ነበር ።
፺፤ አቤቱ ፡ የእስራኤል ፡ ፈጣሪ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ዛሬ ፡
በውነቱ ፡ ልጅን ፡ ተውህልን ።
፺፩፤ አሁንም ፡ በፊትህ ፡ በኃጢአታችን ፡ ጸንተን ፡
እንኖራለን ፡ ስለዚህም ፡ ስለኃጢአታችን ፡ በፊ
ትህ ፡ እንቆም ፡ ዘንድ ፡ አይገባንም ።
፺፪፤ ዕዝራ ፡ በቤተ ፡ መቅደስ ፡ አንፃር ፡ ተንበርክኮ ፡
እየጸለየ ፡ ባለቀሰ ፡ ጊዜ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ያሉ ፡
ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ሴቶችና ፡ ወንዶች ፡ ቆነጃጅቱም ፡
ፈጽመው ፡ ወደርሱ ፡ ተሰበሰቡ ፡ በእስራኤልም ፡
ጽኑ ፡ ለቅሶ ፡ ተደረገ ።
ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ የተወሰደ ፡ የኢያኤል ፡ ፺፫፤
ልጅ ፡ ኢኮንያስ ፡ ዕዝራን ፡ ጠርቶ ፡ በኢየሩሳ
ሌም ፡ ካሉ ፡ ልዩ ፡ ከሚሆኑ ፡ አሕዛብ ፡ ወገን ፡
ሚስት ፡ ያገባን ፡ እኛ ፡ እግዚአብሔርን ፡ በደ
ልን ፡ አለው ።
አሁንም ፡ ይህ ፡ የተናገርሁት ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በእ ፺፬፤
ስራኤል ፡ ዘንድ ፡ አለ ።
ነገር ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ፍርድህ ፡ መጠን ፡ ልዩ ፡ ከሚ ፺፭፤
ሆኑ ፡ ባገር ፡ ካሉ ፡ ከአሕዛብ ፡ ወገን ፡ ያገባናቸ
ውን ፡ ሚስቶቻችንን ፡ ሁሉ ፡ ከልጆቻቸው ፡
ጋራ ፡ ከኛ ፡ አስወጥተን ፡ እንሰዳቸው ፡ ዘንድ ፡
ስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጠርተን ፡ እንማማል ፡
ይህ ፡ ሥራ ፡ በንተ ፡ ላይ ፡ ነውና ፡ እኛም ፡ ካንተ ፡
ጋራ ፡ እንረዳሃለንና ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ትእ
ዛዝ ፡ የሚወዱ ፡ ሰዎችን ፡ ሁሉ ፡ ተነሥተህ ፡
አምላቸው ።
ዕዝራም ፡ ተነሥቶ ፡ የሕዝቡን ፡ ሹማምንት ፡ ፺፮፤
ካህናቱን ፡ ሌዋውያንንም ፡ እስራኤልንም ፡ ሁሉ ፡
አማላቸው ፡ እነርሱ ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ አማላ
ቸው ፡ እነርሳቸውም ፡ ማሉ ።

ምዕራፍ ፡ ፱ ።

ዕዝራም ፡ ከቤተ ፡ መቅደስ ፡ አደባባይ ፡ ተነ ፩፤
ሥቶ ፡ የናሴሩ ፡ ልጅ ፡ ወደሚሆን ፡ ወደ ፡ ዮና ፡
ቤት ፡ ሄዶ ፡ ተቀመጠ ።
ጽኑ ፡ ብዙ ፡ ለሚሆን ፡ ኃጢአታቸውም ፡ እያለ ፪፤
ቀሰ ፡ እህልን ፡ አልበላም ፡ ውኃንም ፡ አልጠ
ጣም ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ከተማረኩበት ፡ ከፋርስ ፡ ከባቢ ፫፤
ሎን ፡ ለተመለሱ ፡ በይሁዳና ፡ በኢየሩሳሌም ፡
ላሉ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ይገኙ ፡
ዘንድ ፡ አዋጅ ፡ ነገሩላቸው ።
እስከ ፡ ሁለት ፡ እስከ ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ያል ፬፤
ተገኙ ፡ ያልደረሱ ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ሥርዓታቸው ፡
በአለቆቻቸው ፡ ቅጣት ፡ ይቀጡ ፡ ከብቶቻቸው
ንም ፡ ይግደሉባቸው ፡ እነርሱንም ፡ ከወገኖቻ
ቸው ፡ ይለዩዋቸው ።
የብንያምና ፡ የይሁዳ ፡ ወገኖችም ፡ ጨረቃ ፡ ፭፤
ሕፀፅ ፡ ባደረገች ፡ ብርሃኗን ፡ ባጣች ፡ በምስተ
ኛው ፡ ቀን ፡ በዘጠኘኛው ፡ ወር ፡ ወሩ ፡ በባተ ፡
በሦስተኛው ፡ ቀን ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ተሰበሰቡ ።
ሁሉም ፡ በቤተ ፡ መቅደስ ፡ አደባባይ ፡ ተቀ ፮፤
መጡ ፡ ክረምት ፡ ነበርና ፡ ስለ ፡ ውርጭ ፡ ጽናት ፡
ይንቀጠቀጡ ፡ ነበር ።
ዕዝራም ፡ ተነሥቶ ፡ ልዩ ፡ ከሚሆኑ ፡ ከአሕዛብ ፡ ፯፤
ወገን ፡ ሚስት ፡ ያገባችሁ ፡ እናንተ ፡ በደላችሁ ፡
በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ኃጢአት ፡ ጨመራችሁ ፡
አላቸው ።
አሁንም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ተገዙ ፡ ያባቶቻች ፰፤
ንንም ፡ ፈጣሪ ፡ አመስግኑት ።
ፈቃዱንም ፡ ፈጽሙ ፡ ልዩ ፡ ወገን ፡ ከሚሆኑ ፡ ፱፤
በኢየሩሳሌም ፡ ካሉ ፡ ከአሕዛብ ፡ ተለዩ ።

፲፤ ሁሉም ፡ ፈጽመው ፡ ጩኸው ፡ እሺ ፡ አንተ ፡
እንዳዘዝኸን ፡ እናደርጋለን ፡ አሉት ።
፲፩፤ ነገር ፡ ግን ፡ ሰዉ ፡ ብዙ ፡ ነው ፡ ጊዜውም ፡ ክረ
ምት ፡ ነው ፡ ፈጥነን ፡ እናደርገው ፡ ዘንድ ፡ አይ
ቻለንም ፡ የሁለት ፡ ቀን ፡ ሥራ ፡ ብቻ ፡ አይደ
ለም ፡ አሉት ፡ በዚህ ፡ ፈጽመን ፡ በድለናልና ።
፲፪፤ አሁንም ፡ ሹማምቱ ፡ ሁሉ ፡ መንደር ፡ መንድ
ረው ፡ የሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡ ልዩ ፡ ከሚሆኑ ፡ ከአሕ
ዛብ ፡ ወገን ፡ ሚስት ፡ ያገቡ ፡ ሰዎች ፡ ተሰብስ
በው ፡ ወጥተው ።
፲፫፤ ስለዚህ ፡ ስላገኘን ፡ መከራ ፡ እግዚአብሔር ፡
ፈርዶ ፡ ያመጣብን ፡ መከራ ፡ ከኛ ፡ ይርቅልን ፡
ዘንድ ፡ በያገራቸው ፡ የሚኖሩትን ፡ ሹማምቱን ፡
አለቆቻቸውንም ፡ ስለዚህ ፡ ስላገኘን ፡ ሥራ ፡
ይቅጠሯቸው ።
፲፬፤ የአብሂል ፡ ልጅ ፡ ዮናታን ፡ የታቃኑ ፡ ልጅ ፡ ኢያ
ዝያስ ፡ እንደዚህም ፡ አንድ ፡ ሆኑ ፡ መጡ ፡ የሰ
ምስ ፡ ልጅ ፡ ሞሰን ፡ የሰበጤዎስ ፡ ልጅ ፡ ሌዊ
ስም ፡ እነርሳቸውም ፡ አንድ ፡ ሆኑ ።
፲፭፤ ተማርከው ፡ ከሄዱበት ፡ ከፋርስና ፡ ከባቢሎን ፡
የተመለሱትም ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ አደረጉ ።
፲፮፤ ካህኑ ፡ ዕዝራም ፡ በገራቸው ፡ ከተሾሙ ፡ ካለ
ቆች ፡ በያገራቸውም ፡ ጸንተው ፡ ከሚኖሩ ፡
ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ስማቸው ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ የሆነ ፡
ሰዎችን ፡ መረጠ ፡ እንዲህም ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡
እስከሥረኛው ፡ ወር ፡ መባቻ ፡ ድረስ ፡ ተቃጠሩ ።
፲፯፤ ልዩ ፡ ከሚሆኑ ፡ ከአሕዛብ ፡ ወገን ፡ ሚስት ፡ ያገቡ ፡
እነዚያም ፡ ሰዎች ፡ በመጀመሪያ ፡ ወር ፡ መባቻ ፡
እንፈታለን ፡ ብለው ፡ ነገራቸውን ፡ ጨረሱ ።
፲፰፤ ከካህናቱም ፡ ወገን ፡ ልዩ ፡ ከሚሆኑ ፡ ከአሕዛብ ፡
ወገን ፡ ሚስት ፡ ያገቡ ፡ ተገኙ ።
፲፱፤ እሊህም ፡ አግብተው ፡ የተገኙት ፡ ካህናት ፡ የኢ
ዮሴዴቅ ፡ ልጅ ፡ የኢዮስያስ ፡ ልጆችና ፡ የማቲ
ለስም ፡ ወንድሞች ፡ አልዓዛርና ፡ ዮረበስ ፡ ዮአ
ዳኖስም ፡ ናቸው ።
፳፤ ሚስቶቻቸውን ፡ ፈተው ፡ ሰደው ፡ ስለ ፡ ኃጢ
አታቸው ፡ መሥዋዕት ፡ ሠዉ ።
፳፩፤ ከኤምርም ፡ ልጆች ፡ ሚስት ፡ ያገቡ ፡ ሐናንያ ፡
ዘብዴስ ፡ ሜኑስ ፡ ሴሜዎስ ፡ ኢያርማየል ፡ አዛ
ርያ ፡ ናቸው ።
፳፪፤ ከፌትርኤልም ፡ ልጆች ፡ ወገን ፡ የመላያስ ፡
ልጅ ፡ ኢልዮኒስ ፡ አስማኤሎስ ፡ የናትናኤሎስ ፡
ሐቂዶስ ፡ አልታሳም ፡ ናቸው ።
፳፫፤ ከሌዋውያንም ፡ ወገን ፡ የዛብያስ ፡ ሳምያስ ፡ አቱ
አቱዎስ ፡ የሚሉት ፡ ቆሮስ ፡ አቃዴዎስና ፡ ዮሐ
ንስ ፡ ናቸው ።
፳፬፤ ግናያቱን ፡ የሚያደርሱ ፡ ካህናትም ፡ ወገን ፡ የበ
ክሮስ ፡ ልጅ ፡ ኤልያስ ፡ ነው ።
፳፭፤ ከሰሎሙም ፡ ወገን ፡ ወልበኔስ ፡ ነው ።
፳፮፤ ከእስራኤልና ፡ ከፎሮስም ፡ ልጆች ፡ ወገን ፡ አግ
ብተው ፡ የፈቱ ፡ ኢየርማዱያስ ፡ መልክያስ ፡
ሚያኤሎስ ፡ ዓዛር ፡ አሲብያስ ፡ ሳኒስ ፡ ናቸው ።
፳፯፤ ከኤላ ፡ ልጆች ፡ ወገን ፡ የሚማኒያስ ፡ የኢያዚ
ሬሎስ ፡ ልጅ ፡ ዘካርያስ ፡ ኢዮአብድዮስ ፡ ኢያ
ሪሞስ ፡ አዑዴዎስ ፡ ናቸው ።
ከዛሞትም ፡ ልጆች ፡ ወገን ፡ ሲደዳስ ፡ ሄሉ ፡ ያሊ ፳፰፤
ሞስ ፡ አታንያስ ፡ ኢያሪሞስ ፡ ሰበቶስ ፡ ዘርዴ
ዎስ ፡ ናቸው ።
ከቤቤም ፡ ልጆች ፡ ወገን ፡ ዮሐንስ ፡ ሐናንያ ፡ ፳፱፤
ዘብዴዎስ ፡ ሐማቴዎስ ፡ ናቸው ።
ከማኒዮም ፡ ልጆች ፡ ወገን ፡ ለሞስ ፡ ማመኩስ ፡ ፴፤
ኢያዴዎስ ፡ ኢያሱብስ ፡ አስሔሎስ ፡ ኢያርሞት ፡
ናቸው ።
ከዓዲም ፡ ልጆች ፡ ናሐቶስ ፡ መሐልያስ ፡ የቀኑ ፴፩፤
ኖስ ፡ ልጅ ፡ ኒዶስ ፡ ቢሰቀስ ፡ ጳስሚስ ፡ ሲአቱል ፡
በልኑስ ፡ ሚናስያስ ፡ ናቸው ።
ከሐናንያም ፡ ልጆች ፡ ኢልዮሳስ ፡ አስያስ ፡ ምል ፴፪፤
ክያስ ፡ ሱብያስ ፡ ስምዖን ፡ ክሰሉማዊ ፡ ናቸው ።
ከአሰሞም ፡ ልጆች ፡ ወገን ፡ መልጠኔዎስ ፡ መጣ ፴፫፤
ቴያስ ፡ በኔዎስ ፡ ኢሊፍላብ ፡ ምናሴ ፡ ሴሚይ ፡
ናቸው ።
ከአበኒ ፡ ልጆችም ፡ ወገን ፡ እርሚያሰሞን ፡ ሰማ ፴፬፤
ኤል ፡ ኢዮኤል ፡ መምዴ ፡ ጴዴያስ ፡ አናስቀ
ሪቢሰን ፡ አናቢበስ ፡ መንጠኒሞስ ፡ አልሐዩስ ፡
በኑስኤልያሊ ፡ ሰማይስ ፡ ሰሊምያስ ፡ ናታንያስ ፡
ናቸው ፡ ከኢዛርያስም ፡ ልጆች ፡ ወገን ፡ ሴሲ ፡
ሲርያ ፡ አዛኤል ፡ ሳማጢስ ፡ ዘምበሪ ፡ ኢዮሴ
ጵስ ፡ ናቸው ።
ከነሐማም ፡ ልጆች ፡ ወገን ፡ ማዚጢያስ ፡ ዘበዲ ፴፭፤
ያስ ፡ ኤዴሴ ፡ ኢዮኤል ፡ በኒያስ ፡ ናቸው ።
ልዩ ፡ ከሚሆኑ ፡ ከአሕዛብ ፡ ወገን ፡ ሚስት ፡ ያገ ፴፮፤
ቡት ፡ ሰዎች ፡ ሚስቶቻቸውን ፡ ሁሉ ፡ ከልጆ
ቻቸው ፡ ጋራ ፡ አስወጥተው ፡ ሰደዱዋቸው ።
በሰባተኛው ፡ ወር ፡ በጥቅምት ፡ የመባቻ ፡ ዕለት ፡ ፴፯፤
ካህናትና ፡ ሌዋውያን ፡ እስራኤልም ፡ በኢየሩሳ
ሌም ፡ በያገራቸው ፡ ተቀመጡ ፡ የእስራኤልም ፡
ልጆች ፡ በየቦታቸው ፡ ተመለሱ ።
በቤተ ፡ መቅደስ ፡ ደጃፍ ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ፴፰፤
ባለው ፡ አደባባይ ፡ ሁሉም ፡ ተሰብስበው ።
አገልጋይ ፡ ጸሐፊ ፡ የሚሆን ፡ ዕዝራን ፡ የእስራ ፴፱፤
ኤል ፡ ፈጣሪ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሙሴ ፡ የሰ
ጠው ፡ ዳግም ፡ ሕግን ፡ አምጥቶ ፡ ያነብላቸው ፡
ዘንድ ፡ አምጣ ፡ አሉት ።
የካህናት ፡ አለቃ ፡ ዕዝራም ፡ በሰባተኛው ፡ ወር ፡ ፵፤
መባቻ ፡ ለሕዝቡ ፡ ለወንዶች ፡ ለሴቶች ፡ ለካህ
ናቱም ፡ ሁሉ ፡ ሥራታቸውን ፡ ይሰሙ ፡ ዘንድ ፡
ዳግም ፡ ሕግን ፡ አምጥቶ ፡ አነበበላቸው ።
በቤተ ፡ መቅደሱ ፡ ደጃፍ ፡ አንፃር ፡ ባለው ፡ ፵፩፤
አደባባይ ፡ በወንዶቹ ፡ ሁሉ ፡ በሴቶቹም ፡ ፊት ፡
ከነግህ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ቀትር ፡ ድረስ ፡ አነበበላ
ቸው ፡ ሁሉም ፡ በዳግም ፡ ሕግ ፡ የተጻፈ ፡ ሥር
ዓታቸውን ፡ በፍጹም ፡ ልቡናቸው ፡ አደመጡ ።
አገልጋይ ፡ የሆነ ፡ ሕጉን ፡ የሚጽፍ ፡ የሆነ ፡ ዕዝ ፵፪፤
ራም ፡ በሠሩት ፡ እንጨት ፡ በወምበር ተቀምጠ ።
መተጢያስን ፡ ሳሙስን ፡ ሐናንያን ፡ አዛርያን ፡ ፵፫፤
ኡርያስን ፡ ሕዝቅያስን ፡ በአልስሞስንም ፡ ከርሱ ፡
ጋራ ፡ በቀኙ ፡ አስቀመጣቸው ።
በግራውም ፡ በኩል ፡ ፈሐልዴዎስን ፡ ሚሳኤ ፵፬፤

ሉን ፡ ሚልክያስን ፡ ሎቃሳብሰንን ፡ ናባሪያን ፡
ዘከርያስን ፡ አስቀመጠ ።
፵፭፤ ዕዝራም ፡ ያንን ፡ ዳግም ፡ ሕግ ፡ ይዞ ፡ በሰዎቹ ፡
ሁሉ ፡ ፊት ፡ ተቀመጠ ፡ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ያከ
ብሩት ፡ ነበር ።
፵፮፤ ዳግም ፡ ሕግንም ፡ ለማንበብ ፡ በገለጠ ፡ ጊዜ ፡
ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ተነሥተው ፡ ቆሙ ፡ አዛርያም ፡
ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ ገናና ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመ
ሰገነው ።
፵፯፤ ሁሉም ፡ ፈጽመው ፡ መለሱለት ፡ እውነት ፡ ነው ፡
እውነት ፡ ነው ፡ አሉ ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ እጃቸ
ውን ፡ ወደሰማይ ፡ ዘርግተው ፡ በምድር ፡ ወድ
ቀው ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሰገዱ ።
፵፰፤ አኑሲ ፡ ሰራቢያስ ፡ ኢያዲኖስ ፡ ኢያቆብስ ፡ ሳብ
ጣያስ ፡ አውጥያስ ፡ ሚሐና ፡ ቀሊጦስ ፡ አዛርያ ፡
ጠዛብዶስ ፡ ሐኒያስ ፡ ፈልጣስ ፡ ሌዋውያን ፡
የሆኑ ፡ እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡
አስተማሯቸው ።
፵፱፤ በነበበላቸው ፡ ጊዜ ፡ ሁሉም ፡ አንድ ፡ ሆነው ፡
ሰሙ ።
፶፤ አጠራጢም ፡ የካህናቱን ፡ አለቃ ፡ ጸሐፊውን ፡
ዕዝራ ፡ ሁሉን ፡ የሚያስተምሯቸው ፡ ሌዋው
ያንንም ።
፶፩፤ ይቺ ፡ ቀን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የተለየች ፡ ቀን ፡
ናት ፡ አላቸው ፡ ዳግም ፡ ሕግም ፡ ሲነበብ ፡
በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ሁሉም ፡ አለቀሱ ።
፶፪፤ ይቺ ፡ ቀን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የተለየች ፡ ናትና ፡
ሒዱችሁ ፡ ምሳችሁን ፡ በልታችሁ ፡ ለሌላቸው ፡
ሰዎች ፡ ምጽዋቱን ፡ ስጡ ፡ አላቸው ።
፶፫፤ እግዚአብሔር ፡ በመከራ ፡ አይጥላችሁምና ፡
አትዘኑ ፡ አላቸው ፡ ሌዋውያንም ፡ ሕዝቡን ፡
ሁሉ ፡ ይቺ ፡ ቀን ፡ የከበረች ፡ ቀን ፡ ናትና ፡ አት
ዘኑ ፡ ብለው ፡ አዘዟቸው ።
፶፬፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ሁሉም ፡ በልተው ፡ ጠጥተው ፡
ተድላ ፡ ደስታ ፡ ሊያደርጉ ፡ ለሌላቸው ፡ ሰዎች ፡
ምጽዋት ፡ ሊሰጡ ፡ ተኈሥተው ፡ ወደ ፡ ቤታ
ቸው ፡ ሔዱ ።
፶፭፤ በተሰበሰቡበት ፡ በታ ፡ ያስተማሩዋቸውንም ፡
ቃል ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ብዙ ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡
ደስ ፡ አላቸው ።





# መ ጽ ሐ ፈ ጦ ቢ ት ።

በፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ በስልምናሶር ፡ ዘመን ፡ የተማረከ ፡ ከንፍታሌም ፡ ወገን ፡ ከተወለደ ፡ ከአሳሒል ፡ ወገን ፡ የተወለደ ፡ የገባኤል ፡ ልጅ ፡ የጦቢት ፡ ልጅ ፡ የጦብያን ፡ ነገር ፡ የሚናገር ፡ መጽሐፍ ፡ ይህ ፡ ነው ። በነገደ ፡ አሴር ፡ ዕጣ ፡ በላይ ፡ ባለች ፡ የገሊላ ፡ ክፍል ፡ በምትሆን ፡ በነገደ ፡ ንፍታሌም ፡ ዕጣ ፡ በምትሆን ፡ በቂድዮስ ፡ ቀኝ ፡ ከምትሆን ፡ ከታቢስም ፡ የተማረከ ፡ የጦቢት ፡ ልጅ ፡ የጦብያን ፡ ነገር ፡ የሚናገር ፡ ይህ ፡ ነው ።

ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ እኔ ፡ ጦቢት ፡ በሕይወት ፡ በኖርሁበት ፡ ዘመን ፡
በሚገባና ፡ በእውነት ፡ ሥራ ፡ ጸንቼ ፡ ኖርሁ ፡ ወደ ፡
ነነዌና ፡ ወደ ፡ ፋርስ ፡ አገር ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ለመጡ ፡
ለወገኖቼ ፡ ብዙ ፡ ምጽዋት ፡ መጸወትሁ ።
፪፤ እኔ ፡ ሕፃን ፡ ሆኜ ፡ በአገሬ ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡
ጋራ ፡ ሳለሁም ፡ ብዙ ፡ ምጽዋት ፡ መጸወትሁ ።
አባቴና ፡ የንፍታሌም ፡ ወገኖች ፡ ሁሉ ፡ እስራ
ኤል ፡ ሁሉ ፡ በርሱ ፡ መሥዋዕት ፡ ይሠዉ ፡ ዘንድ ፡
እግዚአብሔር ፡ ከሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ነገደ ፡ እስራ
ኤል ፡ አገር ፡ በመረጣት ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ከተ
ሠራው ፡ ሕግ ፡ ወጥተው ፡ ካዱ ። በከበረ ፡ ለዘለ
ዓለሙ ፡ ለልጅ ፡ ልጅም ፡ በተሠራላቸው ፡ በከ
በረ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ በቤተ ፡ መቅ
ደስም ፡ ከተሠራው ፡ ሕግ ፡ ወጥተው ፡ ካዱ ።
፫፤ የካዱ ፡ ሰዎችም ፡ ሁሉ ፡ ደማሊ ፡ ለሚባል ፡
ጣዖትና ፡ በዐል ፡ ለሚባል ፡ ጣዖት ፡ መሥዋዕት ፡
ሠዉ ፡ አባቴና ፡ የንፍታሌም ፡ ወገኖችም ፡ ሁሉ ፡
ከነርሳቸው ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ሆኑ ።
እኔ ፡ ግን ፡ ዘላለም ፡ ጸንቶ ፡ በሚኖር ፡ በአሪት ፡ ፬፤
ለእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ በበዓል ፡
ጊዜ ፡ ብቻዬን ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡
እሄድ ፡ ነበር ፡ በመጀመሪያ ፡ ከሸለትሁት ፡ ከበ
ጎቼ ፡ ጸጉር ፡ በመሠዊያው ፡ ላሉ ፡ ለአሮን ፡
ልጆች ፡ ለካህናቱ ፡ እወስድላቸው ፡ ነበር ።
ያሥራቱን ፡ መጀመሪያና ፡ እህሉንም ፡ ሁሉ ፡ ፭፤
ለሚያገለግሉ ፡ ለአሮን ፡ ልጆች ፡ እሰጣቸው ፡
ነበር ፡ የሁለተኛውን ፡ ዘመን ፡ አሥራት ፡ ግን ፡
እሸምተው ፡ ነበር ፡ ምጽዋቱንም ፡ አወጣጥቼ ፡
ባመት ፡ ባመት ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ እሄድ ፡
ነበር ።
ሦስተኛውንም ፡ አሥራት ፡ ያባቴ ፡ እናት ፡ ፮፤
ዲቦራ ፡ እንዳዘዘች ፡ ለድኆች ፡ እሰጥ ፡ ነበር ፡
መጀመሪያውን ፡ አሥራት ፡ አወጣ ፡ ነበር ። ሁለ
ተኛውንም ፡ ዘመን ፡ አሥራት ፡ እሰጥ ፡ ነበር ።
እናትና ፡ አባቴ ፡ በድኅነት ፡ ትተውኛልና ፡ ፯፤
አካለ ፡ መጠን ፡ በደረስሁ ፡ ጊዜ ፡ ከዘመዶቼ ፡
ልጅ ፡ ሚስት ፡ አገባሁ ፡ ከርሷም ፡ ጦብያ ፡ የሚ
ባል ፡ ልጅ ፡ ወለድሁ ።
ወንድሞቼም ፡ ሁሉ ፡ ተማርከው ፡ ወደ ፡ ነነዌ ፡ ፰፤
በሄዱ ፡ ጊዜ ፡ ከዘመዶቼ ፡ ተለይተው ፡ የአሕ
ዛብን ፡ እህል ፡ በሉ ።
እግዚአብሔርን ፡ በፍጹም ፡ ልቡናዬ ፡ አስበዋ ፱፤
ለሁና ፡ የአሕዛብን ፡ እህል ፡ እንዳልበላ ፡ እኔ ፡
ግን ፡ ሰውነቴን ፡ ጠበቅሁ ።
እግዚአብሔርም ፡ በስልምናሶር ፡ ፊት ፡ መወ ፲፤
ደድንና ፡ ባለሟልነትን ፡ ሰጠኝ ፡ እርሱም ፡
አለቃ ፡ አድርጎ ፡ ሾመኝ ።

፲፩፡ ወደ፡ ምድያም፡ ሄድሁ፡ የምድያም፡ ክፍል፡
በምትሆን፡ በራጊስ፡ ያለ፡ ገባኤልንም፡ ገንዘ
ቤን፡ አደራ፡ አስጠበቅሁት ።
፲፪፡ ስልምናሶር፡ በሞተ፡ ጊዜ፡ ሥራው፡ ክፉ፡
የሆነ፡ ሰናክሬም፡ ስለሱ፡ ፈንታ፡ነገሠ ። ከሹ
መቴ፡ ሻረኝ፡ ከዚህም፡ በኋላ፡ ወደ፡ ምድ
ያም፡ መሄድ፡ አልቻልኩም ።
፲፫፡ በስልምናሶርም፡ ዘመን፡ ለወንድሞቼ፡ ብዙ፡
ምጽዋት፡ መጸወትሁ ።
፲፬፡ እህሌንም፡ ለተራቡ፡ ሰዎች፡ ሰጠሁ፡ ልብሴ
ንም፡ ለተራቆቱ፡ ሰዎች፡ ሰጠሁ ። ከወገኖቼ፡
በነነዌ፡ አደባባይ፡ የሞተ፡ ሰውንም፡ ባይ፡ እቀ
ብረው፡ ነበር ።
፲፭፡ ሸሽቶ፡ ከይሁዳ፡ በተመለሰ፡ ጊዜ፡ ሰናክሬም፡
የገደላቸው፡ ሰዎች፡ ቢኖሩ፡ ተቈጥቶ፡ ብዙ፡
ሰው፡ ገድሏልና፡ እኔ፡ ተሠውሬ፡ እቀብራ
ቸው፡ ነበር፡ ንጉሡም፡ ፈልጎ፡ ሬሳቸውን፡
አላገኘም ።
፲፮፡ ከነነዌ፡ አንድ፡ ሰው፡ ሄዶ፡ እንደቀበርኋቸው፡
ነገር፡ ሠርቶ፡ ከንጉሡ፡ አጣላኝ፡ ሊገድሉኝ፡
እንዲፈልጉኝ፡ በወቅሁ፡ ጊዜ፡ ፈርቼ፡ ተሠ
ወርሁ ።
፲፯፡ ባጡኝም፡ ጊዜ፡ ልጄ፡ ጦብያና፡ ሚስቴ፡ ሐና፡
ሲቀሩ፡ ገንዘቤን፡ ሁሉ፡ በረበሩ ።
፲፰፡ ሁለቱ፡ ልጆቹ፡ ሁሉ፡ እስኪገድሉት፡ ድረስ፡
ሸሽተውም፡ ወደ፡ አራራት፡ ተራራ፡ እስኪ
ሄዱ፡ ድረስ፡ ፶፭፡ ቀን፡ ከቤቴ፡ አልወጣሁም ።
ልጁ፡ እስራዶንም፡ ስለርሱ፡ ፈንታ፡ ነገሠ፡
የወንድሜ፡ ልጅ፡ የእናሔል፡ ልጅ፡ አኪአኪ
ሮስንም፡ በሥራታቸውና፡ በበቴ፡ ወገኖች፡
ላይ፡ ሁሉ፡ ሾመው ።
፲፱፡ አኪአኪሮስም፡ ማለደልኝ፡ ወደ፡ ነነዌም፡
መለሰኝ ። በቤቱ፡ ጣጣና፡ ማኅተም፡ ለርሱ፡
ያለ፡ አኪአኪሮስም፡ ዳግመኛ፡ እክሮንድስን፡
ሾመ ።
፳፡ ወደ፡ አገሬም፡ በተመለስሁ፡ ጊዜ፡ ልጄ፡ ጦብ
ያንና፡ ሚስቴ፡ ሐናን፡ መለሰልኝ ።

ምዕራፍ፡ ፪ ።

፩፡ ሰባተኛ፡ ሱባዔ፡ በምትሆን፡ በከበረች፡
በዓለ፡ ፶፡ ለእኔ፡ በጎ፡ ነገር፡ አደረጉ፡ እበላም፡
ዘንድ፡ ተቀመጥኩ ።
፪፡ ፈጽሞ፡ እንደ፡ መሸ፡ በየሁ፡ ጊዜ፡ እግዚአብሔ
ርን፡ አስቤዋለሁና፡ ልጄን፡ ሄደህ፡ ከወንድሞ
ቻችን፡ ያገኘሃቸውን፡ ድኆች፡ ሰዎችን፡ አምጣ፡
እነሆ፡ እኔ፡ እጠብቅሃለሁ፡ አልሁት ።
፫፡ በተመለሰም፡ ጊዜ፡ ከወንድሞቻችን፡ የሞተ፡
አንድ፡ ሰው፡ አገኘሁ፡ ሬሳውም፡ በደባባይ፡
ወድቋል፡ አለኝ ።
፬፡ እኔም፡ እህል፡ ሳልቀምስ፡ ተነሥቼ፡ ፀሐይ፡
እስኪገባ፡ ድረስ፡ ወደ፡ አንዱ፡ ቤት፡ አገባሁት ።
፭፡ ወደ፡ ቤቴ፡ ተመልሼ፡ ቃጥቤ፡ እያዘንሁ፡
ራቴን፡ በላሁ ።
፮፡ አሞፅ፡ በዓላችሁ፡ ወደ፡ ኀዘን፡ ተድላችሁ፡ ደስ
ታችሁም፡ ወደ፡ ልቅሶ፡ ይመለሳል፡ ያለውን፡
አሰብሁ ።
ከዚያ፡ በኋላ፡ አለቀስሁ፡ ፀሐይም፡ በገባ፡ ፯፡
ጊዜ፡ ሔጄ፡ መቃብር፡ ቆፍሬ፡ ቀበርሁት ።
ንጉሥ፡ የገደላቸውን፡ ይቀብራልና፡ ስለዚህ፡ ፰፡
ሥራ፡ እንዳይገድሉት፡ ይህ፡ ሰው፡ አይፈራ
ምን፡ ብለው፡ ሳቁብኝ ።
በዚያችም፡ ሌሊት፡ ኃጢአተኛ፡ ሆኜ፡ በድ ፱፡
ሞው፡ ሥር፡ ተኛቼ፡ አደርኩ፡ ዓይኖቼ፡ ግን፡
ተገልጠው፡ ነበር ።
በድሞው፡ ላይ፡ ወፎች፡ እንዳሉ፡ አላወቅሁም፡ ፲፡
ፊቴ፡ ተገልጦ፡ ሳለ፡ እለዚያ፡ ወፎች፡ በዓይኔ፡
ላይ፡ ትኩስ፡ ፋንድያ፡ ጣሉብኝ፡ በዓይኔ፡ ብልዝ፡
ብጉር፡ ወጣብኝ ። እኔም፡ ወደ፡ ባለ፡ መድኃ
ኒት፡ ሄድኩ፡ ነገር፡ ግን፡ የጠቀመኝ፡ የለም ።
ብቻየን፡ ወደ፡ ኤልማድያ፡ እስክሄድ፡ ድረስ፡
አኪአክሮስ፡ ይመግበኝ፡ ነበር ።
ሐናም፡ በሴቶች፡ ቤት፡ ታገለግል፡ ነበር ። ፲፩፡
ወደ፡ እመቤቶቿ፡ ላከች፡ እነዚያም፡ አንዲት፡ ፲፪፡
የበግ፡ ጠቦት፡ ሰጧት ።
ወደኔ፡ በመጣች፡ ጊዜ፡ ትጮህ፡ ጀመር፡ ይቺን፡ ፲፫፡
ጠቦት፡ ከወዴት፡ አመጣሽት፡ አልኋት ። የተ
ሰረቀ፡ ገንዘብ፡ መብላት፡ አይገባምና፡ የሰረቅ
ሺውም፡ እንደ፡ ሆነ፡ ለጌቶቹ፡ መልሺው፡
አላት ።
ስለ፡ ደሞዜ፡ ፈንታ፡ ሰጡኝ፡ አለችኝ፡ እኔ፡ ፲፬፡
ግን፡ አላመንኋትም፡ ለባለቤቶቹ፡ መልሺ፡
ብዬ፡ ከርሷ፡ ጋራ፡ ተከራከርሁ ። እርሷም፡
መልሳ፡ ምጽዋትህና፡ ጸሎትህ፡ ወዴት፡ ነው፡
እነሆ፡ በላይህ፡ ያለ፡ ኃጢአትህ፡ ሁሉ፡ ታወቀ፡
አለችኝ ።

ምዕራፍ፡ ፫ ።

በልቡናዬ፡ ኀዘን፡ ተከዝሁ፡ ጸለይኩ፡ አለቀ ፩፡
ስሁ ።
አቤቱ፡ በሥራህ፡ ሁሉ፡ በፍርድና፡ በቸርነት፡ ፪፡
በሚገባ፡ እውነትም፡ አንተ፡ እውነተኛ፡ ነህ፡
አልሁ ። አቤቱ፡ አንተ፡ በሚገባ፡ ዓለምን፡ ትገ
ዛለህ ።
አስበህ፡ በዓይኑ፡ ምሕረት፡ ተቀበለኝ፡ አንተን፡ ፫፡
በበደሉ፡ ትእዛዝህንም፡ ባልሰሙ፡ በአባቶቼ፡
ኃጢአትና፡ በኃጢአቴ፡ ተበቀለህ፡ አታጥፋኝ ።
ለመማረክና፡ ለመበርበር፡ ለሞትም፡ አደረግ ፬፡
ኸኝ፡ በዓለሙ፡ ሁሉ፡ በነርሳቸውም፡ ዘንድ፡
በተበተንበቸው፡ በአሕዛብ፡ አገር፡ ተግዳሮት፡
ለመስማት፡ መተረቻ፡ ሆንን ።
አሁንም፡ በእውነት፡ የሚፈረድ፡ ፍርድህ፡ ፭፡
ብዙ፡ ነው፡ ትእዛዝህን፡ አላደረግንምና፡ በፊ
ትህም፡ በውነት፡ ጸንተን፡ አልኖርንምና፡ ያባ
ቶቼና፡ የእኔ፡ ኃጢአት፡ በሚሠረይ፡ ገንዘብ፡
አድርግልኝ ።
አሁንም፡ በፊትህ፡ ደስ፡ የሚያሰኝህን፡ ነገር፡ ፮፡
አድርግ፡ ከመኖር፡ ሞት፡ ይሻለኛልና፡ በሞት፡
እሰናበት፡ ዘንድ፡ መሬትም፡ እሆን፡ ዘንድ፡

ነፍሴን ፡ የሚቀበላት ፡ መልአክ ፡ እዘዝልኝ ።
በሐሰትና ፡ በውርደት ፡ ተግዳሮትን ፡ ሰምቻለ
ሁና ፡ ኃዘን ፡ በዛብኝ ፡ ከመከራዬ ፡ እሰናበት ፡
ዘንድ ፡ ዘላለም ፡ ጸንቶ ፡ ወደሚኖር ፡ ወደ ፡
መቃብር ፡ እሔድ ፡ ዘንድ ፡ እዘዝ ፡ ገጸ ፡ ረድኤ
ትህን ፡ ከኔ ፡ አትመልስ ።
፯፤ የሚዶን ፡ ክፍል ፡ ከሆነች ፡ ከጣኔስ ፡ የተወለደ ፡
የራጉኤል ፡ ልጅ ፡ ሳራን ፡ በዚያች ፡ ቀን ፡ ተግ
ዳሮት ፡ አገኛት ።
፰፤ ለሰባት ፡ ሰዎች ፡ ቢያጋቧት ፡ በሴትና ፡ በወንድ ፡
ልማድ ፡ ሳያቀርቧት ፡ አስማንድዮስ ፡ የሚባል ፡
ክፉ ፡ ጋኔን ፡ ገድሏቸዋልና ፡ ያባቷ ፡ ባሮች ፡
ተገዳደሩባት ። እነሆ ፡ ሰባት ፡ ሰዎች ፡ አገቡሽ ፡
ባሎችሽ ፡ እየታነቁ ፡ እንዲሞቱ ፡ አታውቂምን ፡
አሏት ፡ ከነርሳቸው ፡ አንዱ ፡ ስንኳ ፡ አልቀረሽም ።
፱፤ እነርሳቸው ፡ ሞተዋልና ፡ ምን ፡ ያህል ፡ ይመስ
ልሻል ፡ ከለሳቸው ፡ ጋራ ፡ በሞት ፡ ሒጂ ፡ ካንቺ ፡
የተወለዱ ፡ ሴትና ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ እስከ ፡ ዘለዓ
ለሙ ፡ ድረስ ፡ አንይ ፡ አሏት ።
፲፤ ታንቃ ፡ እስክትሞት ፡ ድረስ ፡ ይህን ፡ በሰማች ፡
ጊዜ ፡ ፈጽማ ፡ አዘነች ፡ ለናትና ፡ ላባቷ ፡ እኔ ፡
አንድ ፡ ነኝ ፡ እንደዚህ ፡ በደርግ ፡ ላባቴ ፡ ተግዳ
ሮት ፡ እሆንበታለሁ ፡ ያረጀ ፡ ሰውነቱንም ፡ በጭ
ንቅ ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ አወርዳታለሁ ።
፲፩፤ በሰገነት ፡ መስኮት ፡ ሆና ፡ ጸለየች ፡ አቤቱ ፡
አንተ ፡ ፈጣሪዬ ፡ የከበርህ ፡ ነህ ፡ የከበረ ፡ ስም
ህም ፡ ይመስገን ፡ ሥራህም ፡ ሁሉ ፡ የተመሰገነ ፡
ነው ፡ ስምህም ፡ ለዘለዓለሙ ፡ የተመሰገነ ፡ ነው ፡
አለች ።
፲፪፤ አቤቱ ፡ አሁንም ፡ ሰውነቶቼን ፡ ለአንተ ፡ ሰጠሁ ።
፲፫፤ እንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ተግዳሮት ፡ እንዳልሰማ ፡
ከዚህ ፡ ዓለም ፡ በሞት ፡ እሰናብተኝ ፡ እልኩሀ ።
፲፬፤ ከሰው ፡ ጋራ ፡ ከሚሠራው ፡ ኃጢአት ፡ ሁሉ ፡
እኔ ፡ ንጹሕ ፡ እንደሆንኩ ፡ አቤቱ ፡ አንተ ፡
ታውቃለህ ።
፲፭፤ በተማረክሁበትም ፡ አገር ፡ ያባቴን ፡ ስም ፡ አላ
ረከስሁም ፡ እኔ ፡ ለአባቴ ፡ አንዲት ፡ ነኝ ፡ የቀ
ረበ ፡ ዘመድ ፡ ወንድምም ፡ የለኝም ፡ ሰባቱ ፡ ሁሉ ፡
ሞተውብኛልና ፡ ለስምንተኛው ፡ ሰው ፡ እጠበ
ቅለታለሁ ፡ ከዚያ ፡ በኋላስ ፡ ለምን ፡ እኖራለሁ ።
ልትገድለኝ ፡ ትወድ ፡ እንደሆነ ፡ በዓይኑ ፡ ምሕ
ረት ፡ ተመልክተህ ፡ ራራልኝ ፡ ተግዳሮት ፡ በል
ሰማ ፡ ገንዘብ ፡ እዘዝልኝ ።
፲፮፤ የሁለቱም ፡ ጸሎታቸው ፡ በእግዚአብሔር ፡ በገ
ነነ ፡ ጌትነቱ ፡ ፊት ፡ ተሰማ ።
፲፯፤ ሁለቱንም ፡ ያድናቸው ፡ ዘንድ ፡ ከጦቢትም ፡
ዓይን ፡ ብልዙን ፡ ያጠፋለት ፡ ዘንድ ፡ ሚስት ፡
ልትሆነው ፡ የራጉኤል ፡ ልጅ ፡ ሳራንም ፡ ለጦ
ቢት ፡ ልጅ ፡ ለጦብያ ፡ ይሰጠው ፡ ዘንድ ፡ ጦብያ ፡
ገንዘብ ፡ ያደርጋታልና ፡ ክፉ ፡ ጋኔን ፡ አስማን
ድዮስንም ፡ ያጠፋው ፡ ዘንድ ፡ ቅዱስ ፡ ሩፋኤ
ልን ፡ ላከው ። በዚያ ፡ ወራት ፡ ጦቢት ፡ ተመ
ልሶ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ገባ ፡ የራጉኤል ፡ ልጅ ፡ ሳራም ፡
ከሰገነት ፡ ወረደች ።

ምዕራፍ ፡ ፬ ።

ጦቢትም ፡ በዚያች ፡ ቀን ፡ በሚዶኑ ፡ ሰው ፡ ፩፤
በገባኤል ፡ ዘንድ ፡ አደራ ፡ ያስጠበቀውን ፡ የብ
ሩን ፡ ነገር ፡ አሰበ ።
እነሆ ፡ ለሙት ፡ ብዬ ፡ አሰብሁ ፡ ልጄን ፡ ጦብ ፪፤
ያን ፡ ጠርቼ ፡ የማልነግረው ፡ ምንድነው ፡ ሳል
ሞት ፡ የማልነግረውስ ፡ ለምንድነው ፡ ብሎ ፡
አሰበ ።
ጠርቶ ፡ ልጄ ፡ በሞትሁ ፡ ጊዜ ፡ አክብረህ ፡ ቅበ ፫፤
ረኝ ። እናትህንም ፡ ጠብቃት ፡ በሕይወትም ፡
በኖርህበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ አክብራት ። የወደ
ደችውንም ፡ አድርግላት ፡ አታሳዝናት ፡ አለው ።
ልጄ ፡ በማኅፀንም ፡ ባንተ ፡ ብዙ ፡ መከራን ፡ ፬፤
እንደ ፡ ተቀበለች ፡ አስብ ፡ ይህን ፡ አስበህ ፡ በሞ
ተችም ፡ ጊዜ ፡ ከኔ ፡ ዘንድ ፡ ባንድ ፡ መቃብር ፡
ቅበራት ፡ አለው ።
ልጄ ፡ በዘመኑ ፡ ሁሉ ፡ ፈጣሪህ ፡ እግዚአብሔ ፭፤
ርን ፡ አስበው ፡ ትእዛዙን ፡ መካድና ፡ በደልን ፡
አትውደድ ፡ በሕይወትም ፡ በኖርህበት ፡ ዘመን ፡
ሁሉ ፡ እውነትን ፡ ሥራ ፡ በበደል ፡ ሥራም ፡
ጸንተህ ፡ አትኑር ።
እውነት ፡ ነገርን ፡ ከሠራሃት ፡ በሠራኸው ፡ ፮፤
ሥራና ፡ በጐዳናህ ፡ ሁሉ ፡ ትከናወናለህ ፡ እው
ነትን ፡ የሠሩዋት ፡ ሰዎችም ፡ ሁሉ ፡ ሥራቸው ፡
ይከናወንላቸዋል ።
ከገንዘብህም ፡ ምጽዋት ፡ ስጥ ፡ ምጽዋትም ፡ ፯፤
በመጸወትህ ፡ ጊዜ ፡ በገንዘብህ ፡ አትዘን ፡ ከድ
ኃም ፡ ፊትህን ፡ አትመልስ ። እግዚአብሔርም ፡
ገጸ ፡ ረድኤቱን ፡ ካንተ ፡ አይመልስም ።
ያለህን ፡ ገንዘብ ፡ የተቻለህን ፡ ያህል ፡ ምጽ ፰፤
ዋትን ፡
ምጽዋት ፡ መመጽወት ፡ ድልብን ፡ ታደልብል ፱፤
ሃለችና ፡ ጥቂቱም ፡ ቢሆን ፡ ምጽዋት ፡ ለመመ
ጽወት ፡ በገንዘብህ ፡ አትዘን ።
ምጽዋት ፡ በመከራ ፡ ቀን ፡ ከሞት ፡ ታድናለችና ፡ ፲፤
ወደ ፡ ጨለማ ፡ ይገቡ ፡ ዘንድ ፡ አታሰናብትም ።
ምጽዋት ፡ ለሚያደርጋትም ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በእ ፲፩፤
ግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ደግ ፡ ስጦታ ፡ ናት ።
ልጄ ፡ ራስህን ፡ ከዝሙት ፡ ጠብቅ ፡ ካባቶችህ ፡ ፲፪፤
ልጆች ፡ ወገን ፡ አስቀድመህ ፡ ሚስት ፡ አግባ ።
ከዘመዶችህ ፡ ከልተወለደች ፡ ከባዕድ ፡ ወገን ፡
ግን ፡ አታግባ ። እኛ ፡ ደጋግ ፡ ከሚሆኑ ፡ ከጥንት ፡
ጀምረው ፡ ከነበሩ ፡ ከአብርሃምና ፡ ከኖኅ ፡ ከያ
ዕቆብና ፡ ከይስሐቅ ፡ የተወለድን ፡ ነንና ፡ ከባዕድ ፡
የተወለደች ፡ አታግባ ። ልጄ ፡ ሁሉም ፡ ከባቶ
ቻቸው ፡ ልጆች ፡ ሚስት ፡ እንዳገቡ ፡ አስብ ፡
ልጆቻቸውም ፡ እንደ ፡ ተባረኩ ፡ የልጅ ፡ ልጆ
ቻቸውም ፡ ምድርን ፡ እንደ ፡ ወረሷት ፡ አስብ ።
ልጄ ፡ አሁንም ፡ ባልንጀራህን ፡ ውደድ ፡ በባል ፲፫፤
ንጀራህም ፡ ልቡናህን ፡ አታኩራ ፡ ከወገኖችህ ፡
ልጆች ፡ ከሴት ፡ ልጆችና ፡ ከወንዶች ፡ ልጆቻ
ቸው ፡ የተወለደች ፡ ልጅን ፡ ሚስት ፡ አግባ ።
ትዕቢት ፡ ካለች ፡ ዘንድ ፡ ውርደት ፡ አለችና ፡

ብዙ ፡ ሁከትም ፡ አለና ፡ ሁከትም ፡ ክለች ፡ ዘንድ ፡
ችጋር ፡ አለች ። የችጋር ፡ መገኛ ፡ ስለ ፡ ሆነች ፡
ሁከትም ፡ ክለች ፡ ዘንድ ፡ ብዙ ፡ ችግርና ፡ ጦም ፡
አዳር ፡ አለችና ፡ ልጄ ፡ በባልንጀራህ ፡ ልቡና
ህን ፡ አታሣራ ።
፲፬ በጊዜዋ ፡ ጊዜ ፡ ስጠው ፡ እንጂ ፡ የተገዛልህ ፡
የምንደኛህ ፡ ደመወዝ ፡ ሁሉ ፡ በንተ ፡ ዘንድ ፡
አይደር ። ለእግዚአብሔር ፡ ከተገዛህ ፡ ዋጋህ ፡
ይበዛልሃል ፡ ለራስህ ፡ እወቅ ፡ በባሕርይህና ፡
በሥራህ ፡ ሁሉ ፡ አዋቂ ፡ ሁን ።
፲፭ ለራስህ ፡ የጠላኸውን ፡ ለማንም ፡ ለማን ፡ አታ
ድርግ ፡ ለመስከር ፡ ወይን ፡ አትጠጣ ፡ ከሰካሮች ፡
ጋራ ፡ በጐዳና ፡ አትሂድ ።
፲፮ ከእህልህ ፡ ለተራበ ፡ ሰው ፡ ስጥ ፡ ከልብስህም ፡
ለተራቆተ ፡ ሰው ፡ ስጥ ፡ የተረፈህንም ፡ ሁሉ ፡
ለምጽዋት ፡ አድርግ ።
፲፯ እህልህንም ፡ በጻድቃን ፡ መቃብር ፡ ላይ ፡ አሳ
ድር ፡ (በድኃ ፡ ሆድ ፡ አሳድር ፡) ለባለጸጎች ፡
ግን ፡ አትስጥ ።
፲፰ ከመምህራን ፡ ዘንድ ፡ ምክርን ፡ ፈልግ ። የምት
ረባህንም ፡ ምክር ፡ አታቃል ።
፲፱ በየጊዜው ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግነው ፡ ጐዳ
ናህ ፡ የቀና ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ወደርሱ ፡ ለምን ፡
በጐዳናህና ፡ በሥራህም ፡ ሁሉ ፡ ይከናወንል
ሃል ። በጎውን ፡ ሁሉ ፡ ምክር ፡ የሚሰጥ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ አሕዛብ ፡ የሚመክሩት ፡
ከእግዚአብሔር ፡ ያልተገኘ ፡ ምክር ፡ ከንቱ ፡
ነውና ፡ ከመምህራን ፡ ምክርን ፡ ፈልግ ። ያዋር
ደው ፡ ዘንድ ፡ የሚወደውን ፡ እርሱ ፡ ያዋርደ
ዋል ። እርሱ ፡ እንደ ፡ ወደደ ፡ ይሆናል ። ልጄ ፡
አሁንም ፡ ትእዛዜን ፡ አስብ ፡ ከልቡናህም ፡ አይ
ጥፋ ።
፳ አሁንም ፡ የሜዶን ፡ ክፍል ፡ በምትሆን ፡ የራ
ጊስ ፡ ሰው ፡ በግብርያል ፡ ልጅ ፡ በገባኤል ፡ ዘንድ ፡
አደራ ፡ ያስጠበቅሁት ፡ ያሥሩን ፡ ብር ፡ ነገር ፡
እነግርሃለሁ ።
፳፩ ድኆች ፡ ክንተ ፡ ዘንድ ፡ ብዙ ፡ በረከትን ፡ ይቀ
በላሉና ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ከፈራኸው ፡ ባንተ ፡
ዘንድ ፡ በረከት ፡ ይገኛልና ፡ ልጄ ፡ ከችጋር ፡
የተነሣ ፡ አትፍራ ፡ ኃጢአትህንም ፡ ሁሉ ፡ ይቅር ፡
ይልሃል ፡ እግዚአብሔርን ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡
ሥራ ፡ በፊቱ ፡ ሥራ ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ ጦብያም ፡ መለሰ ፡ አባቴ ፡ ያዘዝኸኝን ፡ ሁሉ ፡
እሠራለሁ ፡ አለ ።
፪ ነገር ፡ ግን ፡ አገሩን ፡ የማላውቀውን ፡ ያንን ፡
ብር ፡ ማምጣት ፡ እንዴት ፡ እችላለሁ ፡ አለው ።
፫ ደብዳቤ ፡ ሰጠው ፡ ከንተ ፡ ጋራ ፡ የሚሔድ ፡
ሰው ፡ ፈልግ ፡ እኔም ፡ በሕይወት ፡ ሳለሁ ፡ ደመወ
ዙን ፡ እሰጠዋለሁ ፡ ሒደህ ፡ ያንን ፡ ብር ፡ አምጣ ፡
አለው ።
፬ እርሱም ፡ ሰውን ፡ ሊፈልግ ፡ ሒዶ ፡ መልአኩን ፡
ሩፋኤልን ፡ አገኘው ፡ ነገር ፡ ግን ፡ መልአክ ፡
እንደ ፡ ሆነ ፡ አላወቀም ።
አገሩን ፡ ታውቅ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የሜዶን ፡ ክፍል ፡ ፭
ወደምትሆን ፡ ወደ ፡ ራጊስ ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ መሔድ ፡
ትችላለህን ፡ አለው ።
ያም ፡ መልአክ ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ እሔዳለሁ ፡ መን ፮
ገዱንም ፡ አውቀዋለሁ ፡ በገባኤልም ፡ ቤት ፡
ነበርሁ ፡ አለው ።
ጦብያም ፡ ላባቴ ፡ እስክነግረው ፡ ድረስ ፡ ቆየኝ ፡ ፯
አለው ።
መልአኩም ፡ ሒድ ፡ አትቆይ ፡ አለው ፡ አባቱን ፡ ፰
ከኔ ፡ ጋር ፡ የሚሔድ ፡ ሰው ፡ አገኘሁ ፡ አለው ።
ከማንም ፡ ወገን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ካንተም ፡ ጋራ ፡
ለመሔድ ፡ ሰውነቱ ፡ የታመነ ፡ እንደሆነ ፡ አውቅ ፡
ዘንድ ፡ ወደኔ ፡ ጥራው ፡ አለው ።
ጠራው ፡ ገባ ፡ እርስ ፡ በርሳቸውም ፡ እጅ ፡ ተነ ፱
ሣሡ ።
ጦቢትም ፡ አንተ ፡ ወንድሜ ፡ ከማን ፡ ወገን ፡ ፲
ነህ ፡ ከወዴትስ ፡ አገር ፡ መጣህ ፡ አለው ።
መልአኩም ፡ አገሬንና ፡ ወገኔን ፡ ትመረምር ፡ ፲፩
ወይስ ፡ ከልጅህ ፡ ጋራ ፡ የምሔድበትን ፡ ዋጋ ፡
ትሰጠኝ ፡ አለው ፡ ጦቢትም ፡ ስምህንና ፡ ዘመ
ድህን ፡ አውቅ ፡ ዘንድ ፡ እወዳለሁ ፡ አለው ።
እኔስ ፡ የታላቅ ፡ ወንድምህ ፡ የአናንያ ፡ ዘመድ ፡ ፲፪
አዛርያ ፡ ነኝ ፡ አለው ።
አንተ ፡ ወንድሜ ፡ ደኅና ፡ ነህን ፡ አገርህንና ፡ ፲፫
ወገንህን ፡ አውቅ ፡ ዘንድ ፡ መርምሬአለሁና ፡
አገሬንና ፡ ወገኔን ፡ መረመረኝ ፡ ብለህ ፡ አትን
ቀፈኝ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ አንተ ፡ በውነቱ ፡ ከደግ ፡
ከከበረ ፡ ወገን ፡ የተወለድህ ፡ ነህ ፡ እኔም ፡ አና
ንያን ፡ አውቀዋለሁ ፡ አናንያና ፡ ኢታያንን ፡
አውቃቸዋለሁ ፡ የታላቂቱ ፡ የሴምዩ ፡ ልጅ ፡
አዛርያንም ፡ አውቀዋለሁ ፡ አለው ፡ እንሰግድ ፡
ዘንድ ፡ ከነርሳቸው ፡ ጋራ ፡ አብረን ፡ ኢየሩሳ
ሌም ፡ ሒደን ፡ ነበር ፡ የሀላችን ፡ አሥራትና ፡
ከከብቶቻችን ፡ መጀመርያ ፡ የተወለደውን ፡
ወስደን ፡ ነበር ፡ ነገር ፡ ግን ፡ በአባቶቻችን ፡
በደልን ።
አንተ ፡ ግን ፡ ከደግ ፡ አባት ፡ የተወለድህ ፡ ነህ ፡ ፲፬
ነገር ፡ ግን ፡ ንገረኝ ፡ ደመወዝህን ፡ ምን ፡ እንስ
ጥህ ፡ በቀን ፡ በቀን ፡ አንድ ፡ ወቄት ፡ እንሰጥህን ፡
ምግብህስ ፡ ከልጄ ፡ ጋራ ፡ ይሁን ።
በደኅናስ ፡ ከተመለሳችሁ ፡ በደመወዝህ ፡ ላይ ፡ ፲፭
ደመወዝ ፡ እጨምርልሃለሁ ፡ አለው ፡ እንዲህ ፡
ተነጋግረው ፡ ነገራቸውን ፡ ጨረሱ ።
መልአክንና ፡ ጦብያንም ፡ ትሔዱ ፡ ዘንድ ፡ ትከ ፲፮
ናወኑም ፡ ዘንድ ፡ ተዘጋጁ ፡ አላቸው ። ልጁ ፡
ለመንገድ ፡ ስንቃቸውን ፡ አዘጋጀ ። አባቱም ፡
ከዚህ ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ ሒድ ፡ በሰማይ ፡ የሚኖር ፡
እግዚአብሔር ፡ ጐዳናችሁን ፡ ያቅናላችሁ ፡
መልአኩም ፡ አብሮአችሁ ፡ ይሂድ ፡ አለው ፡
ሁለቱ ፡ ሁሉ ፡ ወጥተው ፡ ሔዱ ። ሁለተኛ ፡
ብላቴናም ፡ ተከተላቸው ።
እናቱ ፡ ሐናም ፡ አለቀሰች ፡ በጃችን ፡ ያለ ፡ በፊ ፲፯
ታችን ፡ የሚወጣ ፡ ልጃችን ፡ በጃችን ፡ እንደ ፡

ተያዘ ፡ በትር ፡ ነውና ፡ ልጇን ፡ ለምን ፡ ላክሽው ፡
አለችው ።
፲፰ ብሩስ ፡ እልም ፡ ድርግም ፡ ብሎ ፡ ይጥፋ ።
፲፱ እግዚአብሔር ፡ የሰጠን ፡ የምንድንበት ፡ በእ
ርሱ ፡ ተስፋ ፡ የምንኖርበት ፡ የልጁ ፡ ቤዛ ፡ ይሁን ፡
አለችው ።
፳ ጦቢትም ፡ እኅቴ ፡ ወደኔ ፡ እልፍ ፡ ብለሽ ፡ አት
ናገሪ ፡ በደኅና ፡ ይመለሳል ፡ በዓይኖችሽም ፡
ታይዋለሽ ።
፳፩ ቸር ፡ መልአክ ፡ በፊቱ ፡ ይሄዳልና ፡ ጉዳናው
ንም ፡ ያቃናለታልና ፡ በደኅና ፡ ይመለሳልና ፡
አትዘኚ ፡ አላት ።
፳፪ ሐናም ፡ ልቅሶዋን ፡ ተወች ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ በመንገዳቸውም ፡ ሲሄዱ ፡ ፈሳሽ ፡ ውሀ ፡ ወዳ
ለበት ፡ ወደ ፡ ጤግሮስ ፡ ማታ ፡ ደረሱ ፡ በዚያም ፡
አደሩ ።
፪ ያም ፡ ልጅ ፡ ሊታጠብ ፡ ወረደ ፡ ከወንዙ ፡
ውስጥ ፡ ወጥቶ ፡ ዓሣ ፡ ተወረወረ ፡ ያንንም ፡
ልጅ ፡ ይዘ ፡ ይውጠው ፡ ዘንድ ፡ወደደ ።
፫ መልአኩም ፡ ያንን ፡ ዓሣ ፡ ያዘው ፡ አለው ፡ ያም ፡
ልጅ ፡ ዓሣውን ፡ ወደ ፡ የብስ ፡ አወጣው ።
፬ ያም ፡ መልአክ ፡ ዓሣውን ፡ እረደው ፡ አለው ፡
ጉበቱንና ፡ ልቡን ፡ አሞቱንም ፡ ያዝ ፡ አጥብ
ቀህ ፡ ጠብቀው ።
፭ ያም ፡ ልጅ ፡ መልአኩ ፡ እንዳዘዘው ፡ አደረገ ፡
ዓሣውንም ፡ ጠበሰው ፡ በሉ ። ሁለቱ ፡ ሁሉ ፡
ገሥግሠው ፡ ሄደው ፡ ወደ ፡ በጣኔስ ፡ ደረሱ ።
፮ ያም ፡ ልጅ ፡ መልአኩን ፡ አንተ ፡ ወንድሜ ፡ አዛ
ርያ ፡ የዚህ ፡ ዓሣ ፡ሐሞቱና ፡ ጉበቱ ፡ ለምንድ
ነው ፡ አለው ።
፯ መልአኩም ፡ ክፉ ፡ ጋኔን ፡ ያደረበት ፡ ቢኖር ፡
ወይም ፡ የረከሰ ፡ ረቂቅ ፡ ጋኔን ፡ ያደረበት ፡
ቢኖር ፡ ጉበቱና ፡ ልቡን ፡ ለዚያ ፡ ሰው ፡ በፊቱ ፡
ያጤሱለታል ፡ ሴትም ፡ብትሆን ፡ያጤሱላታል ፡
ከዚያ ፡ በኋላ ፡ አይታመምም ።
፰ ብልዝ ፡ ባለበት ፡ ሰው ፡ አሞቱን ፡ ደቁሰው ፡
ይኩሉታል ።
፱ ወደ ፡ ራጊስም ፡ በደረሱ ፡ ጊዜ ፡ መልአኩ ፡
አንተ ፡ ወንድሜ ፡ ዛሬ ፡ በራጉኤል ፡ ቤት ፡ እና
ድራለን ።
፲ እርሱ ፡ ዘመድህ ፡ ነው ፡ ስሟ ፡ ሳራ ፡ የሚባል ፡
አንዲት ፡ ልጅ ፡ አለችው ፡ የርሷ ፡ ርስት ፡ ይደ
ርስሃልና ፡ሚስት ፡ ልትሆንህ ፡ ይሰጥህ ፡ ዘንድ ፡
የርሷን ፡ ነገር ፡ እናገራለሁ ፡ አለው ።
፲፩ አንተም ፡ ከዘመዶቿ ፡ የተወለድህ ፡ ነህ ፡ ልጂ
ቱም ፡ ያማረች ፡ አዋቂ ፡ ናት ።
፲፪ አሁንም ፡ ስማኝ ፡ ላባቷ ፡ እነግረዋለሁ ፡ ስለ ፡
ሙሴ ፡ሕግ ፡ ራጉኤል ፡ ለሌላ ፡ ሰው ፡ ይሰጣት ፡
ዘንድ ፡ አይወድምና ፡ ከራጊስ ፡ በተመለስን ፡
ጊዜ ፡ በኋላ ፡ እናደርጋለን ፡ ከሰው ፡ ሁሉ ፡ ተለ
ይቶ ፡ ርስቷ ፡ ላንተ ፡ ይደርስሃልና ፡ ለሌላ ፡ ሰው ፡
ከሚሰጣት ፡ ብትሞት ፡ ይወዳል ።

ያም ፡ ልጅ ፡ ይኸን ፡ መልአክ ፡ አንተ ፡ ወንድሜ ፡ ፲፫
አዛርያ ፡ ያቺን ፡ ልጅ ፡ ለሰባት ፡ ሰዎች ፡ እንዳጋ
ቧት ፡ እኔ ፡ ሰማሁ ፡ በሰርግ ፡ ጊዜ ፡ ሁሉም ፡
ሞቱ ።
አሁንም ፡ እኔ ፡ ላባቴ ፡ አንድ ፡ ብቻ ፡ ነኝ ፡ ባገ ፲፬
ባሁ ፡ ጊዜ ፡ የናትና ፡ ያባቴንም ፡ ሰውነት ፡ በጭ
ንቅ ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ እንዳላወርድ ፡ እፈራለሁ ፡
የሚቀብራቸው ፡ ሌላ ፡ ልጅ ፡ የላቸውም ፡ አለው ።
ያም ፡ መልአክ ፡ ከዘመዶችህ ፡ ሚስት ፡ ታገባ ፡ ፲፭
ዘንድ ፡ አባትህ ፡ ያዘዘህን ፡ ቃል ፡ አታስብምን ፡
አለው ። አሁንም ፡ አንተ ፡ ወንድሜ ፡ ስማኝ ፡
ከዘመዶችህ ፡ የተወለደች ፡ እርሷ ፡ በዚህ ፡
ሌሊት ፡ ሚስት ፡ ሆና ፡ ትሰጥሃለችና ፡ የጋኔኑ ፡
ነገር ፡ግን ፡ አያሳዝንህ ።
ወደ ፡ ጫጉላ ፡ ቤት ፡ በገባህ ፡ ጊዜ ፡ የደቀቀ ፡ ፲፮
ዕጣን ፡ ከዚህም ፡ ዓሣ ፡ ከልቡ ፡ ከሆበቱ ፡ አም
ጥተህ ፡ አጢስበት ።
ያንን ፡ ጋኔኑን ፡ በሸተተው ፡ ጊዜ ፡ ይሸሻል ፡ ለዘ ፲፯
ለዓለሙ ፡ አይመለስም ። ወደ ፡ ርሷም ፡ በገባህ ፡
ጊዜ ፡ ሁለታችሁ ፡ ይቅር ፡ባይ ፡ ወደ ፡ ሆነ ፡ ወደ ፡
እግዚአብሔር ፡ ጸልዩ ፡ ይቅር ፡ ብሎ ፡ ያድናች
ኋል ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ አንተን ፡ አዘጋጅቶሃ
ልና ፡ እንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ አትፍራ ፡ አንተ ፡ ታድ
ናታለህ ፡ እርሷም ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ ትሔዳለች ፡
ከርሷም ፡ ልጅ ፡ እንድትወልድ ፡ እነግርሃለሁ ።
ጦብያም ፡ ይህን ፡ ሰምቶ ፡ አደነቀ ፡ ሰውነቱም ፡
እርሷን ፡ አሰበች ፡ ወደ ፡ በጣኔስም ፡ ደረሱ ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

ወደ ፡ ራጉኤል ፡ ቤት ፡ ደረሱ ፡ ሣራም ፡ ተቀ ፩
ብላ ፡ ደስ ፡ አሰኘቻቸው ፡ እንደዚሁ ፡ እነርሳቸ
ውም ፡ እርሷን ፡ ደስ ፡ አሰኟት ፡ ወደ ፡ ቤትም ፡
አገባቻቸው ።
ራጉኤልም ፡ ሚስቱ ፡ አድናን ፡ ይህ ፡ ልጅ ፡ ፪
ድንቅ ፡ ነው ፡ ከዘመዶቹ ፡ የተወለደ ፡ ጦቢትን ፡
ይመስለዋል ፡ አላት ።
ራጉኤልም ፡ ወንድሞቻችን ፡ እናንተ ፡ ከወ ፫
ዴት ፡ መጥታችኋል ፡ አላቸው ፡ እነርሱም ፡ ከን
ፍታሌም ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ ነነዌ ፡ የተማረክን ፡
ነን ፡ አሉት ።
ራጉኤልም ፡ ወንድሜ ፡ ጦቢትን ፡ ታውቁታላ ፬
ችሁን ፡ አላቸው ፡ እናውቀዋለን ፡ አሉት ። ከጉ
ልበት ፡ ነውን ፡ ደኅና ፡ ነውን ፡ አላቸው ።
አዎን ፡ ደኅና ፡ ነው ፡ አሉት ፡ ጦብያም ፡ አባቴ ፡ ፭
ነው ፡ አለው ።
ራጉኤልም ፡ ተወርውሮ ፡ ሳመው ፡ አለቀሰ ። ፮
አንተ ፡ የደግ ፡ ሰው ፡ ልጅ ፡ ነህ ፡ ብሎ ፡ መረ ፯
ቀው ፡ የጦቢትም ፡ ዓይኑ ፡ እንደ ፡ ጠፋ ፡ ነገረው ።
የጦቢትም ፡ ዓይን ፡ እንደ ፡ ጠፋ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡
አዝኖ ፡ አለቀሰ ።
ልጁ ፡ ሣራና ፡ ሚስቱ ፡ አድናም ፡ አለቀሱ ፡ በተ ፰
ድላ ፡ በደስታም ፡ ተቀበሉዋቸው ፡ በግ ፡ አረዱ ፡
ማዕድም ፡ አቀረቡላቸው ፡ አጥብቆ ፡ መሸ ።
ጦብያም ፡ አዛርያን ፡ አንተ ፡ ወንድሜ ፡ አዛርያ ፡

በጕዳና ፡ ያልከኝን ፡ ነገር ፡ ተናገር ፡ ነገሩም ፡
ይለቅ ፡ አለው ፡ ጦብያ ፡ ለመልአኩ ፡ እንደተና
ገረው ፡ ራጉኤል ፡ ይኸን ፡ ሰምቶ ።
፱ ልጄ ፡ ላንተ ፡ ትገባለችና ፡ ራጉኤል ፡ ጦብያን ፡
ብላ ፡ ጠጣ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ደስ ፡ ይበልህ ፡ ብሎ ፡
ተናገረው ፡ አንተም ፡ ታገባታለህ ፡ አለው ።
፲ የዚችን ፡ የልጄን ፡ እውነተኛ ፡ ሥራዋን ፡ እነግ
ርሃለሁ ፡ ለሰባት ፡ ሰዎች ፡ አጋብኋት ፡ ወደርሷ ፡
ከገቡ ፡ በኋላ ፡ ሌሊት ፡ ይሞታሉ ፡ ነገር ፡ ግን ፡
አንድ ፡ ጊዜ ፡ ደስ ፡ ይበልህ ፡ አለው ፡ ጦብያም ፡
ነገሩን ፡ ለኔ ፡ እስክትጨርሱልኝ ፡ ድረስ ፡ ነገሬ
ንም ፡ እስክታጸኑልኝ ፡ ድረስ ፡ በዚህ ፡ በታ ፡
ምንምን ፡ እህል ፡ አልቀምስም ፡ አለው ።
፲፩ ራጉኤልም ፡ አንተ ፡ ወንድሟ ፡ ነህና ፡ እርሷም ፡
እኅትህ ፡ ናትና ፡ እንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ እንደ ፡
ሥርዓቱ ፡ ውሰዳት ፡ ይቅር ፡ ባይ ፡ እግዚአብሔ
ርም ፡ መንገዳችሁን ፡ ያቅናላችሁ ፡ አለው ።
፲፪ ልጁ ፡ ሣራን ፡ ጠራት ፡ እጅዋን ፡ ይዞ ፡ ሚስት ፡
ልትሆነው ፡ ለጦብያ ፡ ሰጣት ፡ እነሆ ፡ በሙሴ ፡
ሥርዓት ፡ ውሰዳት ፡ ወዳባትህም ፡ ቤት ፡ አግ
ባት ፡ ብሎ ፡ መረቃቸው ።
፲፫ ሚስቱ ፡ አድናንም ፡ ጠራት ፡ ጽፎ ፡ ደብዳቤ ፡
አመጣ ፡ አተማት ።
፲፬ ይበሉም ፡ ጀመር ።
፲፭ አድናንም ፡ ጠርቶ ፡ አንቺ ፡ እኅቴ ፡ ሌላ ፡ የጫ
ጕላ ፡ ቤት ፡ አዘጋጂ ፡ ወደዚያም ፡ አግቢያት ፡
አላት ።
፲፮ እንዳዘዛትም ፡ አደረገች ፡ ወደዚያ ፡ አግብታት ፡
የልጅዋን ፡ እንባዋን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
አቀረበች ።
፲፯ ስለዚች ፡ ኀዘንሽ ፡ ፈንታ ፡ የምድርና ፡ የሰማይ ፡
ጌታ ፡ ተድላ ፡ ደስታን ፡ እንዲሰጥሽ ፡ እመኚ ፡
አለቻት ።

ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ ተመግበውም ፡ በጨረሱ ፡ ጊዜ ፡ ጦብያን ፡ እርሷ ፡
ወዳለችበት ፡ ቤት ፡ አገቡት ።
፪ ወደርሷም ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ የሩፋኤልን ፡ ነገር ፡
አሰበ ፡ የደቀቀ ፡ ዕጣን ፡ አምጥቶ ፡ የዚህን ፡
ዓሣ ፡ ጉበቱንና ፡ ልቡን ፡ ጨምሮ ፡ አጤሰው ።
፫ ያም ፡ ጋኔን ፡ መዓዛው ፡ በሸተተው ፡ ጊዜ ፡ እስ
ከላይኛው ፡ ግብጽ ፡ አውራጃ ፡ ድረስ ፡ ሸሸ ፡
ይኸም ፡ መልአክ ፡ ጋኔኑን ፡ አሥሮ ፡ አጋዘው ።
፬ ሁለቱ ፡ ሁሉ ፡ ቤት ፡ በተዘጋባቸው ፡ ጊዜ ፡ ጦብያ ፡
ከአልጋው ፡ ተነሥቶ ፡ እቴ ፡ ተነሽ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ይቅር ፡ ይለን ፡ ዘንድ ፡ እንለምን ፡ አላት ።
፭ ጦብያም ፡ አቤቱ ፡ ያባቶቻችን ፡ ፈጣሪ ፡ አንተ ፡
ምስጉን ፡ ነህ ፡ የከበረ ፡ ስምህም ፡ ይመስገን ፡
ለዘለዓለሙም ፡ ይመሰገናል ። የፈጠርካቸው ፡
ፍጥረትና ፡ ሰማዮችም ፡ ያመሰግኑሃል ፡ ይል ፡
ጀመረ ።
፮ አባታችን ፡ አዳምን ፡ አንተ ፡ ፈጠርከው ፡ ትረ
ዳውም ፡ ታሰርፈውም ፡ ዘንድ ፡ ሔዋንን ፡ ሰጠ
ኸው ፡ ከነዚህም ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ተወለደ ፡ አዳ
ምን ፡ ትረዳው ፡ ዘንድ ፡ ሔዋንን ፡ እንፍጠር
ለት ፡ እንጂ ፡ አዳም ፡ ብቻውን ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡
አንተ ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ አይደለም ፡ አልክ ።
አሁንም ፡ ይህቺን ፡ እቴን ፡ የማገባት ፡ በሚ ፯
ገባ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ስለ ፡ ዝሙት ፡ አይደለምና ፡
አቤቱ ፡ እንረዳዳ ፡ ዘንድ ፡ ለርሷና ፡ ለእኔ ፡ ይቅ
ርታህን ፡ ስደድልን ፡ አለ ።
እርሷም ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ በውነት ፡ ይደረግልን ፡ ፰
አለች ።
በዚያች ፡ ሌሊት ፡ ሁለቱም ፡ አብረው ፡ አደሩ ። ፱
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ራጉኤል ፡ ተነሥቶ ፡ ሔዶ ፡ ፲
እነሆ ፡ እሱም ፡ ወይ ፡ ይሞት ፡ ይሆናል ፡ ብሎ ፡
መቃብር ፡ ቆፈረ ።
ራጉኤልም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ተመለሰ ። ፲፩
ሚስቱ ፡ አድናን ፡ ደኅና ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ሙቶም ፡ ፲፪
እንደሁ ፡ ማንም ፡ ሳያውቅ ፡ እንቀብረው ፡ ዘንድ ፡
አንዲት ፡ ልጅ ፡ ታየው ፡ ዘንድ ፡ ላኪ ፡ አላት ።
ያቺም ፡ ልጅ ፡ ሔዳ ፡ ደጃፉን ፡ ከፈተች ፡ ሁለቱ ፡ ፲፫
ሁሉ ፡ ተኝተው ፡ አገኘቻቸው ።
ተመልሳ ፡ እነሳቸው ፡ ደኅና ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ ነገ ፲፬
ረቻቸው ።
ራጉኤልም ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰገነው ፡ ፲፭
አቤቱ ፡ አንተ ፡ የተመሰገንህ ፡ ነህ ፡ በከበረች ፡
በምትገባ ፡ ምስጋና ፡ ሁሉ ፡ የተመሰገንህ ፡ ነህ ።
በሠራኸው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ጻድቃን ፡ ወዳጆ
ችህ ፡ ያመሰግኑሃል ፡ ወዳጆችህና ፡ አገልጋዮ
ችህ ፡ መላእክትም ፡ ሁሉ ፡ በዓለም ፡ ሁሉ ፡ ያመ
ሰግኑሃል ።
ደስ ፡ አሰኘተኸኛልና ፡ አቤቱ ፡ አቤቱ ፡ አንተ ፡ ፲፮
የተመሰገንህ ፡ ነህ ፡ እንደ ፡ ቸርነትህም ፡ ብዛት ፡
አደረግህልኝ ፡ እንጂ ፡ እንዳሰብኩት ፡ አልተደ
ረገብኝም ።
ሁለቱን ፡ ብቸኞች ፡ ይቅር ፡ ብለሃቸዋልና ፡ በቸ ፲፯
ርነትህ ፡ በደስታና ፡ በደኅንነት ፡ ዘመናቸውን ፡
ይፈጽሙ ፡ ዘንድ ፡ አቤቱ ፡ ቸርነትህን ፡ አድር
ገህላቸዋልና ፡ የተመሰገንህ ፡ ነህ ፡ አለ ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ባሮቹን ፡ ያንን ፡ መቃብር ፡ ይደ ፲፰
ፍኑ ፡ ዘንድ ፡ አዘዛቸው ።
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ አሥራ ፡ አራት ፡ ቀን ፡ በዓል ፡ ፲፱
አደረገላቸው ።
ራጉኤልም ፡ ጦብያን ፡ የሠርጉ ፡ ቀን ፡ የሚሆን ፡ ፳
የአሥራ ፡ አራት ፡ ቀን ፡ በዓል ፡ እስኪፈጸም ፡
ድረስ ፡ ወጥቶ ፡ እንዳይሄድ ፡ አማለው ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ሔዶ ፡ የገንዘቡንም ፡ እኩሌታ ፡ ፳፩
ያመጣ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ አባቱም ፡ በደኅና ፡ ይሄድ ፡
ዘንድ ፡ የተረፈውን ፡ ግን ፡ ሚስቱና ፡ እርሱ ፡
ከሞቱ ፡ በኋላ ፡ ይወስድ ፡ ዘንድ ፡ አማለው ።

ምዕራፍ ፡ ፱ ።

ጦብያም ፡ ሩፋኤልን ፡ ጠርቶ ። ፩
አንተ ፡ ወንድሜ ፡ አዛርያ ፡ ሁለት ፡ ብላቴኖች ፡ ፪
ይዘህ ፡ ግመሎችንም ፡ ጭነህ ፡ የሜዶን ፡ ዕጣ ፡
ወደምትሆን ፡ ወደራጊስ ፡ ከገባኤል ፡ ቤት ፡
ሄደህ ፡ አንድ ፡ መክሊት ፡ ብር ፡ አምጣ ፡ አለው ።

እሱንም ፡ ወደ ፡ በዓሉ ፡ ጥራው ።
፫ ይኸ ፡ በዓሉ ፡ ሳያልቅ ፡ እንዳልወጣ ፡ ራጉኤል ፡
እምለኛልና ።
፬ አባቴ ፡ ግን ፡ ቀን ፡ ይቈጥራል ፡ ብዘገይም ፡
ፈጽሞ ፡ ያዝናል ፡ አለው ።
፭ ሩፋኤልም ፡ ሔደ ፡ በገባኤል ፡ ቤት ፡ አደረ ፡ ደብ
ዳቤውን ፡ ሰጠው ፡ እነዚያም ፡ ስቃዎች ፡ በማ
ኅተማቸው ፡ አምጥቶ ፡ ለሩፋኤል ፡ ሰጠው ።
፮ አንድነት ፡ በጧት ፡ ገሥግሠው ፡ ሔዱ ፡ ወደ ፡
ሠርጉም ፡ ደረሱ ፡ ሩፋኤልም ፡ ያን ፡ ብር ፡ በመ
ጣለት ፡ ጊዜ ፡ ጦብያ ፡ ሩፋኤልን ፡ መረቀው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩ አባቱ ፡ ጦቢት ፡ ግን ፡ ቀን ፡ ይቈጥር ፡ ነበር ።
ቀጠሮው ፡ አልቆ ፡ ሳይመጡ ፡ በቀሩ ፡ ጊዜ ።
፪ ወይ ፡ እነሆ ፡ ልጄ ፡ አፈረን ፡ ወይስ ፡ ገባኤል ፡
ሞቶ ፡ ይሆን ፡ ብሩንስ ፡ የሚሰጠው ፡ ሰው ፡
አጥቶ ፡ ይሆን ፡ አለ ።
፫ አጥብቆ ፡ አዘነ ።
፬ ሚስቱም ፡ ልጄስ ፡ ሞቷል ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡
ቀረ ፡ አለችው ።
፭ ያይኔን ፡ ብርሃን ፡ ልጄን ፡ ያላጠፋሁብኝ ፡ ባይ
ሆን ፡ በላሳዘንኝም ፡ ነበር ፡ ብላ ፡ ታለቅስለት ፡
ጀመር ።
፮ ዝም ፡ በይ ፡ እልፍ ፡ እልፍ ፡ ብለሽ ፡ አትናገሪ ፡
እሱስ ፡ ደኅና ፡ ነው ፡ አላት ።
፯ እሷም ፡ አንተም ፡ ዝም ፡ በል ፡ አታሳንፈኝ ፡
ልጄስ ፡ ሞቷል ፡ አለችው ። ታለቅስለት ፡ ዘንድ ፡
ወደሔደበት ፡ ጐዳና ፡ ሁልጊዜ ፡ ትሔድ ፡ ነበር ፡
ቀን ፡ እህል ፡ አትበላም ፡ ነበር ። የሠርጉ ፡ በዓል ፡
ሳያልቅ ፡ እንዳይሔድ ፡ ራጉኤል ፡ ያማለው ፡
አሥራ ፡ አራት ፡ ቀን ፡ እስኪፈጸም ፡ ድረስ ፡
ለልጅዋ ፡ ለጦብያ ፡ እያለቀሰችለት ፡ ሌሊትም ፡
ዝም ፡ አትልም ፡ ነበር ።
፰ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በዓሉ ፡ ባለቀ ፡ ጊዜ ፡ እናትና ፡
አባቴ ፡ ተስፋ ፡ ቆርጠውልኛልና ፡ እንግዲህ ፡
ወዲህም ፡ ያዩኝ ፡ ዘንድ ፡ ተስፋ ፡ አያደርጉኝ
ምና ፡ ጦብያ ፡ ራጉኤልን ፡ እንግዲህ ፡ ወዲህስ ፡
ልሂድ ፡ አሰናብተኝ ፡ አለው ።
፱ አማቱም ፡ ወሬህን ፡ ይነግሩት ፡ ዘንድ ፡ እኔ ፡
ወደ ፡ አባትህ ፡ እልክለሁ ፡ በኔ ፡ ዘንድ ፡ ተቀ
መጥ ፡ አለው ።
፲ ጦብያም ፡ ወደ ፡ አባቴ ፡ እሔድ ፡ ዘንድ ፡ አሰና
ብተኝ ፡ እንጂ ፡ አይሆንም ፡ አለው ።
፲፩ ራጉኤልም ፡ ተነሥቶ ፡ ሚስቱ ፡ ሣራን ፡ ሰጠው ፡
የገንዘቡን ፡ እኩሌታ ፡ ከብቱንና ፡ ሰውንም ፡
ብሩንም ፡ ሰጠው ።
፲፪ ልጆቼ ፡ ሳልሞት ፡ የሰማይ ፡ ጌታ ፡ በጎ ፡ ነገር ፡
ያድርግላችሁ ፡ ብሎ ፡ መረቃቸው ፡ እንግዲህ ፡
ወዲህ ፡ ዘመድሽ ፡ እርሱ ፡ ነውና ፡ ልጄን ፡ አማ
ትሽን ፡ አክብሪ ፡ አላት ፡ እኛም ፡ ባንቺ ፡ በጎ ፡
ነገር ፡ ተደረገ ፡ ሲባል ፡ እንስማ ፡ ብሎ ፡ ሳማት ።
አድናም ፡ ጦብያን ፡ አንተ ፡ ወንድሚ ፡ የምወ
ደው ፡ የሰማይ ፡ ጌታ ፡ ጐዳናህን ፡ ያቅናልህ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ደስ ፡ ይለኝ ፡ ዘንድ ፡
ከልጄ ፡ ከሣራ ፡ ልጅ ፡ ይስጥህ ፡ አለችው ፡ እን
ዳታሳዝናት ፡ እነሆ ፡ ልጄን ፡ አደራ ፡ ሰጥቼሃለሁ ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ጦብያ ፡ መንገዱን ፡ ሔደ ፡ መን ፲፫
ገዱን ፡ አቅንቶላቿልና ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመ
ሰገነው ፡ ሚስቱ ፡ አድናና ፡ ራጉኤልም ፡ አመ
ሰገኑት ፡ ሔዱ ፡ ወደ ፡ ነነዌም ፡ ቀረቡ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ሩፋኤል ፡ ጦብያን ፡ አንተ ፡ ፩
ወንድሚ ፡ አባትህን ፡ በውርንት ፡ እንደተው
ኸው ፡ አታውቅምን ፡ አለው ።
ና ፡ ከሚስትህ ፡ ቀድመን ፡ ሔደን ፡ ቤቱን ፡ እና ፪
ዘጋጅ ።
የዚህን ፡ ያሣ ፡ አሞት ፡ ያዝ ፡ አለው ፡ ያም ፡ ከነ ፫
ርሳቸው ፡ ጋራ ፡ የተከተለ ፡ ብላቴና ፡ ሔደ ።
ልጅዋን ፡ ታይ ፡ ዘንድ ፡ ሐና ፡ ግን ፡ በጐዳና ፡ ፬
ተቀምጣ ፡ ትመለከት ፡ ነበር ።
ሲመጣም ፡ አይታ ፡ ሔዳ ፡ አባቱን ፡ እነሆ ፭
ልጅህ ፡ መጣ ፡ ከርሱም ፡ ጋራ ፡ የሄደ ፡ ያ ፡ ሰው ፡
መጣ ፡ አለችው ።
ሩፋኤልም ፡ ያባትህ ፡ ዓይኖች ፡ እንዲበሩ ፡ ፮
እኔ ፡ አውቃለሁ ።
አንተ ፡ ግን ፡ ያንን ፡ ሐሞት ፡ ያባትህን ፡ ዓይን ፡ ፯
ኳለው ፡ በተኳለም ፡ ጊዜ ፡ ዓይኖቹን ፡ ያሻል ፡
ያም ፡ ብልዝ ፡ ከይኑ ፡ ይወጣል ፡ ደኅና ፡ ሆኖ ፡
ያያል ፡ አለው ።
ሐናም ፡ ሮጣ ፡ ሔዳ ፡ ልጅዋን ፡ አንገቱን ፡ እቅፍ ፡ ፰
አድርጋ ፡ ይዛ ፡ ልጄ ፡ ከየሁህ ፡ እንግዲህስ ፡
ወዲህ ፡ ልሙት ፡ አለችው ፡ ሁለቱ ፡ ሁሉ ፡
አለቀሱ ።
ጦቢትም ፡ ወደ ፡ ደጅ ፡ ወጣ ፡ ተሰነካከለ ፡ ፱
ልጁም ፡ ሮጦ ፡ አባቱን ፡ አነሣው ።
አባቱን ፡ ያንን ፡ አሞት ፡ ዓይኖቹን ፡ ኳለው ። ፲
እንድትድን ፡ አባቴ ፡ እመን ፡ አለው ።
በተኳለም ፡ ጊዜ ፡ ዓይኖቹን ፡ አሸ ። ፲፩
ያም ፡ ብልዝ ፡ ከይኑ ፡ ብለን ፡ ተገፈፈ ፡ ልጁን ፡ ፲፪
አየው ፡ አንገቱን ፡ እቅፍ ፡ አድርጎ ፡ ይዞ ፡ አለቀሰ ።
አቤቱ ፡ አንተ ፡ የተመሰገንህ ፡ ነህ ፡ ስምህም ፡ ፲፫
ለዘለዓለሙ ፡ ይመስገን ፡ ቅዱሳን ፡ የከበሩ ፡ አገ
ልጋዮችህ ፡ መላእክት ፡ ሁሉ ፡ የተመሰገኑ ፡
ናቸው ፡ በመከራው ፡ ገርፈህ ፡ ይቅር ፡ ብለሽኛ
ልና ፡ ስምህ ፡ ለዘለዓለም ፡ ይመስገን ።
እነሆ ፡ ልጄ ፡ ጦብያን ፡ አየሁት ፡ አለ ፡ ከዚህም ፡ ፲፬
በኋላ ፡ ልጁ ፡ ደስ ፡ እያለው ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ ገባ ፡
ላባቱም ፡ በሚዲን ፡ የተደረገለትን ፡ ታላላቁን ፡
ነገር ፡ ሁሉ ፡ ነገረው ።
ጦቢትም ፡ ደስ ፡ እያለው ፡ ወጥቶ ፡ ምራቱን ፡ ፲፭
ተቀበላት ፡ እግዚአብሔርንም ፡ በነነዌ ፡ አደባ
ባይ ፡ አመሰገነው ፡ ሲሔድም ፡ ያዩት ፡ ሰዎች ፡
እንዲት ፡ አየ ፡ ብለው ፡ አደነቁት ።
እግዚአብሔር ፡ ይቅር ፡ ብሎታልና ፡ ጦቢት ፡ ግን ፡ ፲፯
በፊታቸው ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ተገዛ ፡ ጦቢትም ፡
ወደ ፡ ምራቱ ፡ ወደ ፡ ሣራ ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ ልጄ ፡

በደኅና ፡ ገባሽን ፡ ብሎ ፡ መረቃት ፡ ወደኛ ፡ ያገ
ባሽ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ይመስገን ፡ እናትና ፡
አባትሽንም ፡ ያክብራቸው ፡ አላት ። በነነዌ ፡
ለሚኖሩ ፡ ለወንድሞቹ ፡ ሁሉ ፡ ብዙ ፡ ተድላ ፡
ደስታ ፡ ተደረገ ።
፲፯፡ አኪአክሮስም ፡ መጣ ፡ የወንድሙ ፡ ልጅ ፡ ነሳበ
ስም ፡ መጣ ።
፲፰፡ በተድላ ፡ በደስታ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ በዓል ፡ አደረጉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩፡ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ጦቢት ፡ ጦብያን ፡ ጠርቶ ፡
ልጄ ፡ ከንተ ፡ ጋራ ፡ ለሄደ ፡ ለዚህ ፡ ሰው ፡ ደመ
ወዙን ፡ አይተህ ፡ ስጠው ፡ ዳግመኛም ፡ ትጨ
ምርለት ፡ ዘንድ ፡ ይገባል ፡ አለው ።
፪፡ ጦብያም ፡ አባቱን ፡ ወዳንተ ፡ በደኅና ፡ መልሶ
ኛልና ፡ ሚስቴንም ፡ ፈውሷታልና ፡ ብሩንም ፡
አምጥቶልኛልና ።
፫፡ እንደዚሁም ፡ ሁሉ ፡ አንተንም ፡ ፈውሶሃልና ፡
የገንዘቤን ፡ እኩሌታ ፡ ስንኳ ፡ ብሰጠው ፡ የሚ
ጐዳኝ ፡ የለም ፡ አለው ።
፬፡ አባቱም ፡ እውነት ፡ ተናገርክ ፡ አለው ።
፭፡ ያንንም ፡ መልአክ ፡ ጠርቶ ፡ ከናንተ ፡ ጋራ ፡ ያመ
ጣሁትን ፡ የገንዘቡን ፡ እኩሌታ ፡ ሁሉ ፡ ይዘህ ፡
በተድላ ፡ በደስታ ፡ ሒድ ፡ አለው ።
፮፡ ሩፋኤልም ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ሁለቱን ፡ ሁሉ ፡
ጦብያንና ፡ ጦቢትን ፡ ጠርቶ ፡ ቆይታ ፡ አድርጎ ፡
እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑት ፡ አላቸው ፡ ለር
ሱም ፡ ተገዙ ፡ ለስሙም ፡ ምስጋና ፡ አቅርቡ ፡
ስላደረገላችሁ ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በሰው ፡ ሁሉ ፡
ፊት ፡ እመኑበት ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግ
ኑት ፡ ስሙንም ፡ አመስግኑ ፡ የእግዚአብሔ
ርን ፡ ክብር ፡ ሥራ ፡ በክብር ፡ ተናገሩ ፡ ተአም
ራቱንም ፡ ግለጡ ፡ ለርሱ ፡ መገዛትንም ፡ ቸል ፡
አትበሉ ።
፯፡ የመንግሥትን ፡ ምሥጢር ፡ ሊሠውሩት ፡ የእ
ግዚአብሔርን ፡ ሥራ ፡ ግን ፡ በክብር ፡ ሊገል
ጡት ፡ ይገባልና ፡ አከባብራችሁ ፡ ግለጹት ፡ መከ
ራም ፡ እንዳታገኛችሁ ፡ በጎ ፡ ሥራን ፡ ሥሩት ።
፰፡ ጸሎት ፡ ከምጽዋትና ፡ ከፍቅር ፡ ከሃይማኖትም ፡
ነገር ፡ ጋራ ፡ ያማረ ፡ የተወደደ ፡ ነው ፡ ሠርቆ ፡
ቀምቶ ፡ ከጠራቀሙት ፡ ከብዙ ፡ ገንዘብ ፡ በእው
ነት ፡ ያጠራቀሙት ፡ ጥቂት ፡ ገንዘብ ፡ ይሻላል ።
፱፡ ምጽዋት ፡ ከሞት ፡ ታድናለችና ፡ ከኃጢአትም ፡
ሁሉ ፡ ታነፃለችና ፡ ወርቅ ፡ ከማድለብ ፡ ምጽ
ዋት ፡ መስጠት ፡ ይሻላል ፡ ምጽዋትና ፡ ጽድቅ
ንም ፡ የሚያደርጉ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ለራሳቸው ፡
ሕይወትን ፡ ያገኛሉ ።
፲፡ የሚበድሉ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ሰውነታቸውን ፡
ይጠፏታል ።
፲፩፡ እነሆ ፡ ነገሩን ፡ ሁሉ ፡ ከእናንተ ፡ አልሠውርም ፡
የመንግሥትን ፡ ምሥጢር ፡ ሊሠውሩት ፡ ያማረ ፡
ነው ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ተአምራት ፡ ግን ፡
በክብር ፡ ሊገልጡት ፡ ይገባል ፡ አላችኋለሁ ።
፲፪፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ ምራትህ ፡ ሣራና ፡ አንተ ፡
በጸለያችሁ ፡ ጊዜ ፡ የልመናችሁን ፡ ነገር ፡ ወደ ፡
እግዚአብሔር ፡ አደረስሁ ፡ አንተም ፡ ሬሳ ፡ በቀ
በርህ ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ ነበርኩ ።
ቸል ፡ ብልህ ፡ ጊዜ ፡ ምሳህንም ፡ ትተህ ፡ በተነ ፲፫፡
ሣህ ፡ ጊዜ ፡ ሬሳንም ፡ ትቀብር ፡ ዘንድ ፡ በሔ
ድህ ፡ ጊዜ ፡ በጎ ፡ ሥራንም ፡ መሥራት ፡ ባልዘ
ነጋኸው ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ ነበርኩ ።
ገኸ ፡ ፈጣሪ ፡ የሚሆን ፡ እግዚአብሔርም ፡ አን ፲፬፡
ተን ፡ አድንህ ፡ ዘንድ ፡ ምራትህ ፡ ሣራንም ፡
ከኀዘኗ ፡ አረጋጋት ፡ ዘንድ ፡ ላከኝ ።
የቅዱሳንን ፡ ጸሎት ፡ ከሚያሳርጉ ፡ ወደ ፡ ከበረ ፡ ፲፭፡
ወደ ፡ ገነነ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጌትነትም ፡
ከሚያገቡ ፡ ከከበሩ ፡ ከ፯ ፡ አለቆች ፡ አንዱ ፡
አለቃ ፡ እኔ ፡ ሩፋኤል ፡ ነኝ ፡ አላቸው ።
ይኸንንም ፡ ሰምተው ፡ ሁለቱ ፡ ሁሉ ፡ ደነገጡ ፡ ፲፮፡
ፈርተዋልና ፡ በግምባራቸው ፡ ፍግም ፡ ብለው ፡
ወደቁ ።
ፈጣሪያችሁ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፍሩት ፡ እንጂ ፡ ፲፯፡
እኔን ፡ አትፍሩኝ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፈጽማችሁ ፡
አመስግኑ ።
የፈጣሪያችሁ ፡ ፈቃዱ ፡ አመጣኝ ፡ እንጂ ፡ ምስ ፲፰፡
ጋና ፡ ለእኔ ፡ አይገባኝምና ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ለዘ
ለዓለሙ ፡ በዘመናችሁም ፡ እግዚአብሔርን ፡
አመስግኑት ።
እኔ ፡ ግን ፡ ተገለጥሁላችሁ ፡ መልኬንም ፡ አያ ፲፱፡
ችሁ ፡ ከእናንተ ፡ ጋራ ፡ አልበላሁም ፡ አልጠጣ
ሁም ።
ወደ ፡ ላከኝ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እወጣለሁና ፡ ፳፡
አሁንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ እመኑ ፡ ይህንን ፡
ሁሉ ፡ በመጻፍ ፡ እጽፍ ፡ ዘንድ ፡ መጣሁ ፡ አለ ።
የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ተነሥቶ ፡ ሔደ ፡ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ፳፩፡
አላዩትም ።
ገናና ፡ ድንቅ ፡ በሚሆን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፳፪፡
ሥራ ፡ በተገለጠላቸው ፡ እግዚአብሔር ፡ በላ
ከው ፡ መልአክም ፡ አመኑ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

ጦቢትም ፡ የተድላ ፡ የደስታ ፡ ነገርን ፡ ጻፈ ፡ ፩፡
ለዘለዓለሙ ፡ ሕያው ፡ የሚሆን ፡ ጌትነቱም ፡
ለዘለዓለሙ ፡ ጸንቶ ፡ የሚኖር ፡ እግዚአብሔር ፡
ይመስገን ፡ አለ ።
እሱ ፡ በመከራ ፡ ይገርፋል ፡ ይቅር ፡ ይላል ፡ እሱ ፡ ፪፡
ወደ ፡ ሲኦልም ፡ ያወርዳል ፡ ከሲኦልም ፡ ያወ
ጣል ፡ ከሥልጣኑ ፡ የሚያመልጥ ፡ የለም ፡ አለ ።
የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ በነርሳቸው ፡ ዘንድ ፡ ፫፡
በበተነን ፡ በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ተገዙለት ።
በዚያም ፡ ገናንነቱን ፡ ገለጠ ፡ እሱ ፡ ጌታችን ፡ ፬፡
ነውና ፡ እርሱ ፡ እግዚአብሔር ፡ በዓለሙ ፡ ሁሉ ፡
አባታችን ፡ ፈጣሪያችን ፡ ነውና ፡ በሰው ፡ ሁሉ ፡
ፊት ፡ አክብሩት ፡ አግኑት ።
በኃጢአታችን ፡ ይቀሥፈናል ፡ ዳግመኛም ፡ ፭፡
ይቅር ፡ ይለናል ፡ በነርሳቸውም ፡ አገር ፡ ከበተ
ነን ፡ ከአሕዛብም ፡ አገር ፡ ይሰበስበናል ።
በፊቱ ፡ እውነት ፡ ሥራን ፡ እንሠራ ፡ ዘንድ ፡ ፮፡

በፍጹም ፡ ሰውነታችን ፡ በቅንም ፡ ልቡናችን ፡
ወደሱ ፡ ከተመለስን ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ እሱ ፡ በረ
ድኤት ፡ ወደኛ ፡ ይመለሳል ። ገጹ ፡ ረኤድቱን ፡
ከኛ ፡ አይሠውርም ፡ ለኛ ፡ ያደረገልን ፡ ተአም
ራቱንም ፡ ታያላችሁ ። በፍጹም ፡ ሰውነታች
ሁና ፡ በፍጹም ፡ ልቡናችሁም ፡ እመኑበት ፡ ቸር ፡
እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑት ፡ የዓለሙ ፡ ሁሉ ፡
ንጉሥ ፡ እግዚአብሔርን ፡ በተማረከችሁበት ፡
አገር ፡ አግኑት ፡ አክብሩት ፡ እኔም ፡ በተማረ
ክሁበት ፡ አገር ፡ አምንበት ፡ ነበር ፡ ኃጢአተ
ኞች ፡ ለሆኑ ፡ ለአሕዛብም ፡ ኃይሉን ፡ ገናንነ
ቱን ፡ እነግር ፡ ነበር ። ኃጢአተኞች ፡ ተመልሳ
ችሁ ፡ በፊቱ ፡ ጽድቅን ፡ ሥሩት ፡ ወዶ ፡ ቸር
ነቱን ፡ ለናንተ ፡ ያደርግላችሁ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
ማን ፡ ያውቃል ።
፯፤ ፈጣሪዬን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደርገዋለሁ ። ሰውነ
ቴም ፡ የሰማዩን ፡ ንጉሥ ፡ እግዚአብሔርን ፡
ታመሰግነዋለች ።
፰፤ ገናንነቱንም ፡ በሁሉ ፡ ዘንድ ፡ እናገራለሁ ።
፱፤ የከበርሽ ፡ የኢየሩሳሌም ፡ አገር ፡ በእውነት ፡
እመኝበት ። በልጆችሽ ፡ ኃጢአት ፡ በመከራ ፡
አይቀሥፍሽም ፡ ዳግመኛም ፡ ደጋግ ፡ ለሆኑ ፡
ልጆችሽ ፡ ይራራላቸዋል ።
፲፤ በበጎ ፡ ሥራ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ተገገር ፡ በንቺ ፡
ዘንድ ፡ ደብተራ ፡ አሪት ፡ በተድላ ፡ በደስታ ፡
እንድትሠራ ፡ የዓለሙ ፡ ሁሉ ፡ ንጉሥ ፡ እግዚ
አብሔርን ፡ አመስግኚው ፡ በዚያ ፡ ያሉ ፡ የተማ
ረኩም ፡ ሰዎች ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
፲፩፤ ብዙ ፡ የሆኑ ፡ አሕዛብ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡
አምነው ፡ ከሩቅ ፡ አገር ፡ ያመጣሉና ፡ የተወ ፡
ሰዎች ፡ ለሰማይ ፡ ጌታ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡
መንሻን ፡ ያመጣሉ ፡ በልጅ ፡ ልጅ ፡ ዘመንም ፡
ያመሰግኑሃል ፡ ለስምህም ፡ ምስጋናን ፡ ያቀር
ባሉ ፡ ስላንተ ፡ ጸንተው ፡ ለዘለዓለም ፡ በሚኖሩ ፡
ልጆች ፡ ዘንድ ፡ ይወደዳሉ ።
፲፪፤ የሚጠሉህ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ የተረገሙ ፡ ናቸው ፡
የሚወዱህ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ ለዘለዓለሙ ፡
የተመረቁ ፡ ናቸው ።
፲፫፤ ይሰበሰባሉና ፡ በደጋግ ፡ ሰዎች ፡ ልጆች ፡ ደስ ፡
ይልሃል ፡ የሚወዱህ ፡ ሰዎች ፡ የተደነቁ ፡ ናቸ
ውና ፡ አቤቱ ፡ አንተን ፡ ያመሰግኑሃል ፡ በፍቅር ፡
አንድነትም ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
፲፬፤ ተአምራትህን ፡ ሁሉ ፡ አይተው ፡ በንተ ፡ ደስ ፡
ይላቸዋልና ፡ ስለ ፡ መከራህ ፡ የሚያዝኑ ፡ ሰዎች ፡
ሁሉ ፡ የተደነቁ ፡ ናቸው ፡ ለዘለዓለሙም ፡ ደስ ፡
ይላቸዋል ።
፲፭፤ ኢየሩሳሌም ፡ መረግድ ፡ በሚባል ፡ ዕንቍና ፡
በከበረ ፡ ዕንቍ ፡ ትሠራለችና ፡ ሰውነቴ ፡ ገናና ፡
የሚሆን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ታመሰግነዋለች ።
፲፮፤ ድልድልዋ ፡ ኖራዋ ፡ አደባባዩዋ ፡ በከበረ ፡
ዕንቍ ፡ በጠራም ፡ ወርቅ ፡ ይሠራልና ።
፲፯፤ የኢየሩሳሌም ፡ አደባባዩዋም ፡ ብሬሌ ፡ በሚ
ባል ፡ ዕንቍ ፡ ይሠራልና ፡ አትራክስም ፡ በሚ
ባል ፡ ዕንቍ ፡ ሰፎርም ፡ በሚባል ፡ ዕንቍ ፡
ይሠራልና ።
በጐዳናዋ ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ምስጋና ፡ ፲፰፤
ይገባዋል ፡ ይላሉ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለዘለዓለሙ ፡
ይመስገን ፡ እያሉ ፡ በዓለሙ ፡ ሁሉ ፡ ያመሰግናሉ ።

ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ጦቢት ፡ ከሚጸልየው ፡ ጸሎት ፡ ፩፤
ዝም ፡ አለ ፡ ዓይኑ ፡ በጠፋ ፡ ጊዜ ፡ ፶፰ ፡ ዘመን ፡
ሆኖት ፡ ነበር ።
ከ፶፰ ፡ ዘመን ፡ በኋላ ፡ አየ ፡ ምጽዋት ፡ መጸወተ ፡ ፪፤
ገዥ ፡ የሚሆን ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ፈጽሞ ፡
ፈራ ፡ በርሱም ፡ አመነ ።
ፈጽሞ ፡ አረጀ ፡ ልጁንና ፡ የልጁንም ፡ ልጆች ፡ ፫፤
ጠራቸው ፡ አርጅቻለሁና ፡ ለሞትም ፡ ደርሻለ
ሁና ፡ ልጆችህን ፡ አምጣቸው ፡ አለው ።
ትጠፋ ፡ ዘንድ ፡ እንዳላት ፡ ነቢዩ ፡ ዮናስ ፡ በነነዌ ፡ ፬፤
የተናገረው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ እንዳይቀር ፡ አውቃ
ለሁና ፡ ልጄ ፡ ወደ ፡ ሜዶን ፡ ሂድ ፡ አለው ፡ በሚ
ዶን ፡ ግን ፡ እስከ ፡ ዘመኑ ፡ ድረስ ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡
ይደረጋል ፡ ወንድሞቻችንም ፡ ከከበረች ፡ አገር ፡
ሁሉ ፡ ይበተኑ ፡ ዘንድ ፡ አላቸው ፡ ኢየሩሳ
ሌምም ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ትሆናለች ፡ በርሷም ፡
ያለ ፡ ?እግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ ቤተ ፡ መቅ
ደስ ፡ በእሳት ፡ ይቃጠላል ፡ እስከ ፡ ዘመኑም ፡
ድረስ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ይሆናል ።
ዳግመኛ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይቅር ፡ ብሎ ፡ ወዳገ ፡ ፭፤
ራቸው ፡ ይመልሳቸዋል ፡ ማደሪያው ፡ ቤተ ፡
መቅደስንም ፡ ይሠራሉ ፡ የዘመኑ ፡ ቍጥር ፡
እስከሚፈጸም ፡ ድረስ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ እንደ ፡
ቀድሞው ፡ አይደለም ፡ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ከተማ
ረኩበት ፡ አገር ፡ ይመለሳሉ ፡ ኢየሩሳሌምን ፡
በክብር ፡ ይሠሯታል ፡ በርሷም የእግዚአብ
ሔር ፡ ማደሪያ ፡ ቤተ ፡ መቅደስን ፡ እስከ ፡ ልጅ ፡
ልጅ ፡ ዘመን ፡ ድረስ ፡ በዕብነ ፡ ሩካም ፡ ይሠራሉ ።
አሕዛብም ፡ ሁሉ ፡ በውነት ፡ ወደርሱ ፡ ይመለሳሉ ፡ ፮፤
እግዚአብሔርንም ፡ ይፈሩታል ፡ ጣዖቶቻቸው
ንም ፡ ይጥላሉ ።
አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመሰግኑ ፡ ፯፤
ታል ። ሕዝቡም ፡ በርሱ ፡ ያምናሉ ፡ እግዚአብ
ሔርም ፡ ወገኖቹን ፡ ያገናቸዋል ፡ ያከብራቸዋል ።
በሚገባና ፡ በውነት ፡ ገገር ፡ የሚሆን ፡ እግዚአብ
ሔርን ፡ የሚፈሩ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ ይላቸ
ዋል ፡ ለወንድሞቻቸውም ፡ ቸርነትን ፡ ያደር
ጋሉ ።
ነቢዩ ፡ ዮናስ ፡ የተናገረው ፡ ነገር ፡ ያለውድ ፡ ፰፤
በግድ ፡ ይደረጋልና ፡ ልጄ ፡ አሁንም ፡ ከነነዌ ፡
ውጣ ።
አንተ ፡ ግን ፡ ትእዛዙንና ፡ ሕጉን ፡ ጠብቅ ፡ ይቅር ፡ ፱፤
ባይም ፡ ሁን ፡ በጎ ፡ ረድኤት ፡ ትደረግልህ ፡
ዘንድ ፡ እውነትንም ፡ ውደድ ።
በሞትሁም ፡ ጊዜ ፡ አክብረህ ፡ ቀብረኝ ፡ እና ፡ ፲፤
ትህንም ፡ እንደ ፡ እኔ ፡ አክብረህ ፡ ቀብራት ።
ልጄ ፡ በነነዌ ፡ አትኑር ። ሐማ ፡ በዘመድህ ፡ በአ
ኪአክሮስ ፡ ያደረገው ፡ ክብርሃንም ፡ ወደ ፡ ጨለማ ፡

እንዳገባው፡ ፍዳውንም ፡ እንደ ፡ ተቀበለ ፡ አኪ
አክሮስም ፡ እንደ ፡ ዳነ ፡ እይ ። እርሱ ፡ ግን ፡ ፍዳ
ውን ፡ ተቀበለ ፡ እርሱ ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ወረደ ።
ምናሴ ፡ ምጽዋት ፡ መጸወተ ፡ እውነትንም ፡ አደ
ረገ ፡ ከመከሩበት ፡ ከሞት ፡ መቅሠፍትም ፡ ዳነ ።
ሐማ ፡ ግን ፡ በዚያች ፡ በመከራት ፡ ምክር ፡ ጠፋ ፡
ሞተ ።
፲፩ ልጄ ፡ ምጽዋት ፡ የምታደርገውን ፡ እይ ፡ ከሞት ፡
ታድናለች ፡ ታጸድቃለችም ፡ አለው ። ጦቢት ፡
ይህን ፡ ተናግሮ ፡ ሞተ ፡ በልጋው ፡ ላይ ፡ ሳለ ፡
ነፍሱም ፡ ከሥጋው ፡ ተለየች ። በሞተ ፡ ጊዜ ፡
፻፶ ፡ ስምንት ፡ ዘመን ፡ ሆኖት ፡ ነበር ።
፲፪ አክብረው ፡ ቀበሩት ፡ እናቱ ፡ ሐናም ፡ በሞተች ፡
ጊዜ ፡ ከባቱ ፡ ጋራ ፡ ቀበራት ። ጦብያ ፡ ከልጆ
ቹና ፡ ከሚስቱ ፡ ጋራ ፡ ራጉኤል ፡ ወዳለበት ፡
ወደ ፡ ባጥና ፡ ሄደ ።
፲፫ ሚስቱ ፡ አድናና ፡ ራጉኤልም ፡ አርጅተው ፡
ሞቱ ። አማቶቹንም ፡ አክብሮ ፡ ቀበራቸው ።
ገንዘባቸውን ፡ ሁሉ ፡ ወረሰ ። ያባቱ ፡ የጦቢት
ንም ፡ ገንዘብ ፡ ወረሰ ።
፲፬ ጦብያም ፡ በመቶ ፡ ሐያ ፡ ሰባት ፡ ዘመን ፡ ሞተ ፡
የሜዶን ፡ ክፍል ፡ በምትሆን ፡ በባጥናም ፡ ተቀ
በረ ።
፲፭ አባቱም ፡ እንደ ፡ ነገረው ፡ ሳይሞት ፡ የነነዌን ፡
ጥፋት ፡ ሰማ ። ስልምናሶርና ፡ ናቡከደነፆርም ፡
የነነዌን ፡ ጥፋት ፡ ሰምተው ፡ ደስ ፡ አላቸው ።
ለእግዚአብሔር ፡ ለዘለዓለሙ ፡ በውነት ፡ ያለ ፡
ሐሰት ፡ ክብር ፡ ምስጋና ፡ ይግባውና ፡ ልጁ ፡
ጦብያና ፡ ጦቢት ፡ የተናገሩት ፡ ነገር ፡ መላ ፡
ተፈጸመ ።





# መጽሐፈ ፡ ዮዲት ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ በባጥና ፡ ለሚዶን ፡ በነገሠ ፡ በአርፋስክድ ፡
ዘመን ፡ ከፍ ፡ ባለች ፡ በነነዌ ፡ አገር ፡ ለፋርስ ፡
የነገሠ ፡ ናቡከደነፆር ፡ በነገሠ ፡ ባ፲፪ኛው ፡ ሁለተ
ኛው ፡ ዓመት ።
፪፤ በለዘበ ፡ ደንጊያ ፡ የባጥናን ፡ የድልድሏን ፡ ዙሪያ ፡
ሠራ ፡ በከበሮ ፡ ቤቱ ፡ በኩል ፡ ያለው ፡ የመሠ
ረቷ ፡ ስፋት ፡ ሠላሳ ፡ ክንድ ፡ ነው ፡ ባደባበይዋ ፡
በኩል ፡ ያለው ፡ የድልድሉ ፡ ስፋት ፡ ስድሳ ፡
ክንድ ፡ ነው ፡ የእድሞውንም ፡ ቁመት ፡ ፸ ፡
ክንድ ፡ አድርጎ ፡ ሠራ ፡ ደጀ ፡ ሰላሙም ፡ አምሳ ፡
ክንድ ፡ ነው ።
፫፤ ባደባበዩ ፡ ያለ ፡ እድሞውን ፡ መቶ ፡ መቶ ፡ ክንድ ፡
አልፎ ፡ ሠራ ፡ መሠረቱም ፡ ከማዕዘን ፡ እስከ ፡
ማዕዘን ፡ ድረስ ፡ ስድሳ ፡ ክንድ ፡ ነው ።
፬፤ የሚከፈቱ ፡ የበሯን ፡ ደጃፎች ፡ ሠሩ ፡ ቁመታ
ቸው ፡ ሰባ ፡ ክንድ ፡ አርበኞቹ ፡ ሠራዊትና ፡
የጋኑ ፡ ኃይለኞች ፡ የሚገቡባቸው ፡ የበሮቹ ፡
ወርድ ፡ ሠላሳ ፡ ክንድ ፡ ነው ።
፭፤ ናቡከደነፆር ፡ በዚያ ፡ ወራት ፡ ንጉሡ ፡ አርፋስ
ክድን ፡ በሰፊ ፡ ሜዳ ፡ ተዋጋው ፡ ያም ፡ ምድረ ፡
በዳ ፡ በራግው ፡ አውራጃ ፡ ያለ ፡ ነው ።
፮፤ ባምባ ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎችም ፡ ሁሉ ፡ ወጥተው ፡
ተቀበሉት ፡ በጤግራንና ፡ በኤፍራጥስ ፡ በሐዴ
ስጵንም ፡ ያሉ ፡ በኤሉሚዎን ፡ ንጉሥ ፡ በአር
ዮክ ፡ግዛት ፡ አውራጃ ፡ ያሉ ፡ ሁሉ ፡ ተቀበሉት ፡
የከሉድን ፡ ልጆች ፡ ይዋጓቸው ፡ ዘንድ ፡ እጅግ ፡
ብዙ ፡ የሆኑ ፡ አሕዛብም ፡ ተሰበሰቡ ።
፯፤ የፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆርም ፡ በፋርስ ፡ አው
ራጃ ፡ ወደሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡ በደማስቆና ፡ በቂል
ቅያ ፡ አውጃራ ፡ በሊባኖስም ፡ ወደሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡
በጰራልያም ፡ ወደሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ላከ ።
፰፤ በገለዓድና ፡ በቀርሚሎስ ፡ ሰፊ ፡ በሆነ ፡ በእስ
ዶራንም ፡ ምድረ ፡ በዳና ፡ በገሊላም ፡ ወደሚ
ኖሩ ፡ አሕዛብ ።
በአውራጃዋና ፡ በሰማርያ ፡ ወደሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ፱፤
ሁሉ ፡ ወደ ፡ ዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ እስከ ፡ ኢየሩሳ
ሌም ፡ ድረስ ፡ ላከ ፡ ወደ ፡ ኪሉስና ፡ ወደ ፡ ቢላ
ጢንም ፡ እስከ ፡ ግብጽ ፡ ወንዝ ፡ ድረስ ፡ ወደ ፡
ቃዴስም ፡ ወደ ፡ ራሚስና ፡ ወደ ፡ ጣፍናስም ፡
ወደ ፡ ጌሴም ፡ አገርም ፡ ሁሉ ።
ወደ ፡ ሚኒዎስም ፡ እስከ ፡ ኢትዮጵያ ፡ አው ፲፤
ራጃ ፡ ድረስ ፡ በግብጽ ፡ ወደሚኖሩ ፡ ሰዎችም ፡
ሁሉ ፡ ላከ ።
ባገር ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎችም ፡ ሁሉ ፡ የፋርስ ፡ ፲፩፤
ንጉሥ ፡ የናቡከደነፆርን ፡ ትእዛዝ ፡ እምቢ ፡ አሉ ፡
አልፈሩትምና ፡ በፊታቸውም ፡ እንደ ፡ አንድ ፡
ሰው ፡ ሆኗልና ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ ጦር ፡
አልሔዱም ፡ መልእክተኞቹም ፡ ተዋርደው ፡
ከፊታቸው ፡ ባዶአቸውን ፡ ተመለሱ ።
ናቡከደነፆርም ፡ በዚያች ፡ አገር ፡ ፈጽሞ ፡ ተቈጣ ፡ ፲፪፤
የደማስቂኒስና ፡ የቂልቅያን ፡ የሶርያንም ፡ አው
ራጃ ፡ ሁሉ ፡ ተበቅሎ ፡ በሰይፍ ፡ ያጠፋቸው ፡
ዘንድ ፡ በሞዓብ ፡ አገር ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎችንም ፡
ሁሉ ፡ የአሞንንም ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ ሁለቱም ፡
አገር ፡ አውራጃ ፡ እስኪደርስ ፡ ድረስ ፡ የግብጽ ፡
ሰዎችና ፡ የይሁዳን ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ያጠፋቸው ፡
ዘንድ ፡ የጌትነቱን ፡ ዙፋን ፡ ይንሳኝ ፡ ብሎ ፡ ማለ ።
ከሠራዊቱ ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ ንጉሡ ፡ አርፋስክድን ፡ ፲፫፤
በነገሠ ፡ ባ፲፯ ፡ ሰባተኛው ፡ ዘመን ፡ ተዋጋው ፡
ድል ፡ ነሥቶ ፡ የአርፋስክድን ፡ ገንዘቡን ፡ ሁሉ ፡
ሠረገላዎቹንና ፡ ፈረሶቹን ፡ ሁሉ ፡ ወሰደ ።
አገሮቹንም ፡ ሁሉ ፡ ገንዘብ ፡ አደረገ ፡ እስከ ፡ ፲፬፤
ባጥናም ፡ ድረስ ፡ ሄዶ ፡ አምባቸውን ፡ ያዘ ፡ አገ
ሩን ፡ ሁሉ ፡ በረበረ ፡ አጠፋት ።
አርፋስክድንም ፡ በራግው ፡ አውራጃ ፡ ይዞ ፡ ፲፭፤
በጦር ፡ ወጋው ፡ ፈጽሞም ፡ አጠፋው ።

፲፮፤ እርሱ ፡ ተመለሰ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ያሉ ፡ እጅግ ፡
አርበኞች ፡ የሆኑ ፡ ብዙ ፡ ሰዎችም ፡ ሁሉ ፡ ተመ
ለሱ ፡ ሲያስብ ፡ ሲመክር ፡ በዚያም ፡ አራት ፡
ወር ፡ ተቀመጠ ።

ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩፤ ናቡከደነፆር ፡ በነገሡ ፡ በሥራ ፡ በዐሥራ ፡ ስምንተኛው ፡
ዘመን ፡ በመጀመሪያው ፡ ወር ፡ በሚያዝያ ፡
ጨረቃ ፡ ብርሃኑን ፡ ባጣ ፡ በሰባተኛው ፡ ቀን ፡
አጠፋለሁ ፡ ብሎ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ አገሩን ፡
ሁሉ ፡ ያጠፋ ፡ ዘንድ ፡ በፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ በናቡ
ከደነፆር ፡ ቤት ፡ ምክር ፡ ተመከረ ።
፪፤ ሹማምንቱንና ፡ አለቆቹን ፡ ሁሉ ፡ ጠርቶ ፡ ከነር
ሳቸው ፡ ጋራ ፡ የምክሩን ፡ ምሥጢር ፡ ተነጋገረ ፡
በገሩ ፡ ሁሉ ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡ ተናገረ ።
፫፤ በንደበቱ ፡ በተናገረው ፡ ነገር ፡ ያልተዘጋጁ ፡ ሰዎ
ችን ፡ ሁሉ ፡ ያጠፋቸው ፡ ዘንድ ፡ እነርሳቸውም ፡
ምክር ፡ ጨረሱ ።
፬፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ የፋርሱ ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆር ፡
ምክር ፡ በጨረሱ ፡ ጊዜ ፡ ከርሱ ፡ በታች ፡ ያለ ፡
ቢትወደዱ ፡ ሆሎፎርኒስን ፡ ጠራው ።
፭፤ ያገሩ ፡ ሁሉ ፡ ጌታ ፡ ገናና ፡ የሆነ ፡ ንጉሥ ፡ እን
ዲህ ፡ አለው ፡ አሥር ፡ እልፍ ፡ ከሁለት ፡ ሺ ፡
የሆኑ ፡ በኃይላቸው ፡ የታመኑ ፡ እግረኞች ፡ ሰዎ
ችን ፡ በፈረስ ፡ የተቀመጡ ፡ አሥር ፡ እልፍ ፡ ከሁ
ለት ፡ ሺ ፡ ሰዎችንም ፡ ከፈረሶቻቸው ፡ ጋራ ፡
ከንተ ፡ ጋራ ፡ ይዘህ ፡ እነሆ ፡ ከፊቴ ፡ ትወጣለህ ።
፮፤ በንደበቴ ፡ ለተናገርሁት ፡ ነገር ፡ መታዘዝን ፡
እምቢ ፡ ብለዋልና ፡ በምዕራብ ፡ በኩል ፡ ወዳ
ለች ፡ አገር ፡ ትወጣለህ ።
፯፤ በነርሱ ፡ ተቈጥቼ ፡ እወጣለሁና ፡ ምድርንም ፡
በሠራዊቴም ፡ ብዛት ፡ እሸፍናታለሁና ፡ ገንዘባቸ
ውንም ፡ እዘርፋቸዋለሁ ፡ እበረብራቸዋለሁና ፡
ውኃውንና ፡ አገሩን ፡ ያዘጋጁልኝ ፡ ዘንድ ፡ ለነር
ሳቸው ፡ አዋጅ ፡ ትነግራለህ ።
፰፤ ሬሳቸውም ፡ በውራጃቸው ፡ ሁሉ ፡ በወንዙም ፡
በፈሳሹ ፡ ሁሉ ፡ ይመላል ።
፱፤ ምርኳቸውንም ፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡
እበትነዋለሁ ።
፲፤ አንተ ፡ ግን ፡ ቀድመህ ፡ አውራጃውን ፡ ሁሉ ፡
ያዝልኝ ፡ ራሳቸውን ፡ ወዳንተ ፡ ይመልሱ ፡
ታጠፋቸው ፡ ዘንድ ፡ በገሩም ፡ ትበረብራቸ
ውም ፡ ዘንድ ፡ የከዱትን ፡ ሰዎች ።
፲፩፤ ዓይንህ ፡ አትራራላቸውምና ፡ ተበቅዬ ፡ እስከማ
ጠፋበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ጠብቅልኝ ።
፲፪፤ እኔ ፡ ሕያው ፡ ነኝ ፡ እንደተናገርሁ ፡ ይኸንን ፡
በጄ ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ መንግሥቴም ፡ የጸና ፡
ነው ።
፲፫፤ እንዳዘዝኩህ ፡ አድርግ ፡ እንጂ ፡ አንተም ፡ ከኔ ፡
ከጌታህ ፡ ቃል ፡ አንዲት ፡ ስንኳ ፡ የምትተወው ፡
አይኑር ፡ ይኸንንም ፡ ፈጥነህ ፡ አድርግ ፡ አታስ
ቀር ፡ አለው ።
፲፬፤ ሆሎፎርኒስም ፡ ከጌታው ፡ ፊት ፡ ወጥቶ ፡ ኃይለ
ኞቹን ፡ ሁሉ ፡ ኃይል ፡ ያላቸው ፡ አለቆችንና ፡
የሠራዊቱን ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡ አርበኞውንም ፡
ጠራቸው ።
ያርበኞቹና ፡ የተመረጡት ፡ ሰዎች ፡ ጌታው ፡ ፲፭፤
እንደተናገረ ፡ ቍጥራቸው ፡ እግረኞች ፡ አሥር ፡
እልፍ ፡ ከሁለት ፡ ሺ ፡ ፈረሰኞች ፡ አሥር ፡ እልፍ ፡
ከሁለት ፡ ሺህ ፡ ፍላፃ ፡ የያዙትም ፡ አሥር ፡
እልፍ ፡ ከሁለት ፡ ሺ ፡ ነው ።
ፈጽመው ፡ ይዋጉ ፡ ዘንድ ፡ አዘዛቸው ። ፲፮፤
ስንቃቸውን ፡ የሚጭኑባቸው ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ ፲፯፤
የሆኑ ፡ ግመሎችና ፡ አህዮችን ፡ በቅሎችንም ፡
ምግብ ፡ ሊሆኗቸው ፡ ቍጥር ፡ የሌላቸው ፡
ላሞችና ፡ በጎችን ፡ ፍየሎችንም ፡ ወሰዱ ።
ለብዙ ፡ ሰዎችና ፡ ለሠራዊቱ ፡ ሁሉ ፡ ከንጉሡ ፡ ፲፰፤
ቤት ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡ የሆነ ፡ ብርና ፡ ወርቅን ፡
ስንቅ ፡ አድርጎ ፡ ሰጣቸው ።
እርሱ ፡ ወጣ ፡ ሠራዊቱም ፡ ሁሉ ፡ ወጡ ፡ ሰል ፲፱፤
ፍን ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ በፈረሶችና ፡ በሠረገላ
ዎች ፡ በተመረጡ ፡ አርበኞችም ፡ በምዕራብ ፡
አንፃር ፡ ያለ ፡ ምድርን ፡ ሁሉ ፡ ይሸፍን ፡ ዘንድ ፡
ወጥቶ ፡ ከንጉሡ ፡ አስቀድሞ ፡ ተዋጋ ።
ከነርሳቸው ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ የሆኑ ፡ ብዛታቸው ፡ ፳፤
እንደ ፡ አንበጣ ፡ እንደ ፡ ባሕር ፡ አሸዋም ፡ የሆኑ ፡
ከነርሶቸው ፡ ጋራ ፡ ወጡ ። ከብዛታቸውም ፡ የተ
ነሣ ፡ ቍጥር ፡ የላቸውም ።
ከነነዌ ፡ ወጥተው ፡ በቊጤሊት ፡ ባለ ፡ ምድረ ፡ ፳፩፤
በዳ ፡ አንፃር ፡ የሦስት ፡ ቀን ፡ ጎዳና ፡ ሔዱ ፡ በቂ
ልቅያ ፡ በላይ ፡ ባለ ፡ በግራው ፡ አንፃር ፡ ባለ ፡
ከተራራው ፡ አጠገብ ፡ ከለ ፡ ከበቊጤሊት ፡
ሔዱ ።
ሠራዊቱን ፡ ሁሉ ፡ ፈረሰኞችንና ፡ እግረኞችን ፡ ፳፪፤
ሠረገላዎቹንም ፡ ይዞ ፡ ከዚያም ፡ ወደ ፡ አውራ
ጃቸው ፡ ሔደ ።
ሉድንና ፡ ሬድንም ፡ ወጋቸው ፡ የራስስን ፡ ፳፫፤
ልጆች ፡ ሁሉ ፡ በኤሊም ፡ ግራ ፡ አንፃር ፡ ባለ ፡
ምድረ ፡ በዳ ፡ የሚኖሩ ፡ የእስማኤልንም ፡
ልጆች ፡ ማረካቸው ።
ኤፍራጥስም ፡ ተሻግሮ ፡ ወደ ፡ መስጴጦምያ ፡ ፳፬፤
ሔደ ፡ ወደ ፡ አገር ፡ እስኪደርስ ፡ ድረስ ፡ ደርሶ ፡
አራቱ ፡ አገሮች ፡ ላይ ፡ ያሉ ፡ ከፍ ፡ ያሉ ፡ አም
ባዎችንም ፡ ሁሉ ፡ አፈረሰ ።
የቂልቅያን ፡ አውራጃ ፡ አገኘ ፡ ጠላቱንም ፡ ፳፭፤
ሁሉ ፡ አጠፋ ፡ በምዕራብ ፡ አንፃር ፡ በግራው ፡
በኩል ፡ እስከለ ፡ እስከ ፡ ያፌት ፡ አውራጃም ፡
ድረስ ፡ ሔደ ።
የምድያምን ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ከበባቸው ፡ ከብ ፳፮፤
ታቸውን ፡ ዘረፈ ፡ ቤታቸውንም ፡ አቃጠለ ።
በስንዴ ፡ አዝመራ ፡ ጊዜ ፡ በደማስቆ ፡ ወዳለ ፡ ፳፯፤
ምድረ ፡ በዳ ፡ ወርዶ ፡ አዝመራቸውን ፡ ሁሉ ፡
አቃጠለ ፡ መንጋቸውንና ፡ በጎቻቸውን ፡ ግን ፡
ይዘርፏቸው ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፡ አምባቸውንም ፡
አፈረሰ ፡ ልጆቻቸውን ፡ ማረከ ፡ ጐልማሶቻቸ
ውን ፡ ሁሉ ፡ በጦር ፡ ገደለ ።
እርሱን ፡ መፍራት ፡ ተደረገች ፡ በጺራልያ ፡ በሚ ፳፰፤
ኖሩ ፡ ሰዎች ፡ በጢሮስና ፡ በሲዶና ፡ በሚኖሩ ፡

በአቴናና ፡ በሲይርም ፡ በሚኖሩ ፡ በናሆንም ፡
በሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ድንጋፄ ፡ መጣች ፡ በአስቀ
ሎናና ፡ በአዛጦንም ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ከርሱ ፡
መምጣት ፡ የተነሣ ፡ ፈጽመው ፡ ፈሩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩፤ እነሆ ፡ እኛ ፡ የገናናው ፡ ንጉሥ ፡ የናቡከደነ
ፆር ፡ ባሮች ፡ ነን ፡ በፊትህ ፡ እንኖራለን ።
፪፤ በፊትህ ፡ እንደ ፡ ወደድህ ፡ አድርገን ፡ ብለው ፡
በፍቅር ፡ ቃል ፡ መልክትን ፡ ላኩ ።
፫፤ እነሆ ፡ አገሮቻችን ፡ አምባዎቻችንም ፡ ሁሉ ፡
እርሻችንም ፡ ሁሉ ፡ መንጋዎቻችንም ፡ የመሰ
ማሪያችን ፡ በቃዎች ፡ ሁሉ ፡ በጎቻችንም ፡ በፊ
ትህ ፡ ያንተ ፡ ገንዘቦች ፡ ናቸው ፡ እንደ ፡ ወደ
ድህ ፡ አድርግ ።
፬፤ እነሆ ፡ ታላላቆች ፡ አገሮቻችንም ፡ በነርሳቸው ፡
የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ባሮችህ ፡ ናቸው ፡ መጥተህ ፡
እንደ ፡ ወደድህ ፡ አድርግ ፡ ብለው ፡ ላኩ ።
፭፤ እነዚያም ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡ ሆሎፎርኒስ ፡ ደርሰው ፡
ይህንን ፡ ነገር ፡ ነገሩት ።
፮፤ እርሱም ፡ ወደ ፡ መንደራቸው ፡ ወረደ ፡ ሠራዊ
ቱም ፡ ወረዱ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያሉ ፡ አምባዎችንም ፡
አስጠበቀ ፡ ከነርሳቸውም ፡ የሚረዱት ፡ የተመ
ረጡ ፡ ሰዎችን ፡ ወሰደ ።
፯፤ ወገኖቻቸው ፡ ሁሉና ፡ እነርሳቸውም ፡ አክሊል ፡
ደፍተው ፡ በዘፈን ፡ በገና ፡ እየደረደሩ ፡ ከበሮ ፡
እየመቱ ፡ ተቀበሉት ።
፰፤ እርሱም ፡ አውራጃቸውን ፡ ሁሉ ፡ ዘረ ፡ ጣዖታቻ
ውንም ፡ ሰበረ ፡ ናቡከደነፆርም ፡ ብቻ ፡ እንዲያ
መልኩት ፡ እርሱ ፡ የሰውን ፡ ሁሉ ፡ ጣዖት ፡
ያጠፉ ፡ ዘንድ ፡ የታዘዘ ፡ ነው ። አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡
ሰዎችም ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲሉት ፡
ያጠፉም ፡ ዘንድ ፡ የታዘዘ ፡ ነው ።
፱፤ ከፍ ፡ ባለ ፡ በይሁዳ ፡ ክፍል ፡ በሚሆን ፡ በጸራ
ልያ ፡ አንፃር ፡ የገባኢያ ፡ ዕፃ ፡ ወደሚሆን ፡
ወደ ፡ ኤስድራሲሙም ፡ መጣ ።
፲፤ በሴቅቶን ፡ አገሮችና ፡ በጤባን ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡
መክከልም ፡ሔደ ፡ ለሠራዊቱ ፡ ስንቅ ፡ ያዘጋጅ ፡
ዘንድ ፡ በዚያም ፡ አንድ ፡ ወር ፡ ተቀመጠ ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩፤ በይሁዳ ፡ የሚኖሩ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡
የፋርሱ ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆር ፡ ቢትወደዱ ፡
ሆሎፎርኒስ ፡ በአሕዛብ ፡ ያደረገውን ፡ ሁሉ ፡
አውራጃቸውን ፡ ሁሉ ፡ እንዳጠፋ ፡ እነርሳቸው
ንም ፡ እንዳጠፋቸው ፡ ሰሙ ።
፪፤ ከነገደ ፡ ይሁዳ ፡ የተመረጡ ፡ ወገኖች ፡ ሁሉ ፡
ከተማረኩ ፡ በኋላ ፡ ፈጥነው ፡ ወጥተው ፡ አሉና ፡
ከፊቱ ፡ የተነሣ ፡ ስለ ፡ ፈጣሪያቸው ፡ ስለ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ማደሪያ ።
፫፤ ስለ ፡ ቤተ ፡ መቅደስና ፡ ስለ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡
እጅግ ፡ ፈጽሞ ፡ ፈሩ ። ምሥዋዑንና ፡ ንዋየ ፡
ቅድሳቱን ፡ ቤተ ፡ መቅደሱንም ፡ ካደፈ ፡ በኋላ ፡
አነጹት ።

ወደ ፡ ቆናስና ፡ ወደ ፡ ሰማርያ ፡ ወደ ፡ በልሞ ፬፤
ንና ፡ ወደ ፡ ቤቴሮን ፡ ወደ ፡ አስከባንና ፡ ወደ ፡
ኪያሪን ፡ ወደ ፡ አውሊናሴሌምና ፡ ወደ ፡ አስራ ፡
አውራጃ ፡ ሁሉ ፡ ላከ ።
ከፍ ፡ ከፍ ፡ ወዳሉ ፡ አምባዎቻቸውና ፡ ወደ ፡ ፭፤
አውራጃዎቻቸውም ፡ ራሶች ፡ ሁሉ ፡ ደረሰ ፡
በሚኖሩባቸውም ፡ አገሮች ፡ ላይ ፡ ሰፈሩ ። በዝ
መራቸው ፡ ጊዜ ፡ ድንገት ፡ መጥቶባቸዋልና ፡
ለመዋጋት ፡ ስንቃቸውን ፡ ይዘው ፡ ሄዱ ።
በዚያ ፡ ወራት ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የሚኖር ፡ የካ ፮፤
ህናት ፡ አለቃ ፡ ኢዮአቄም ፡ በዶታይም ፡ አጠ
ገብ ፡ ባሉች ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ በኢያሪኮ ፡ አንፃር ፡
ባሉች ፡ በቤጠሚስቴምና ፡ በቤጤልዋ ፡ ለሚ
ኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ጻፈ ።
በዚያ ፡ በይሁዳ ፡ ላይ ፡ መግቢያ ፡ አለና ፡ መንገ ፯፤
ድን ፡ ትከለክላቸው ፡ ዘንድ ፡ ጐዳናውና ፡ መግ
ቢያው ፡ ምንም ፡ ጠባብ ፡ ቢሆን ፡ የሁለት ፡
ሰዎች ፡ ጐዳና ፡ ብቻ ፡ ትታችሁ ፡ ጨርሳችሁ ፡
አምባውን ፡ ናዱት ፡ ብሎ ፡ ጻፈ ።
የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ካህኑ ፡ ኢዮ ፰፤
አቄም ፡ እንዳዘዛቸው ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ የሚ
ኖሩ ፡ የእስራኤል ፡ ወገኖች ፡ አለቆችም ፡ ሁሉ ፡
እንዳዘዝዋቸው ፡ አደረጉ ።
የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ከፍ ፡ ባለ ፡ ቃል ፡ ወደ ፡ ፱፤
እግዚአብሔር ፡ጮሁ ፡ ሰውነታቸውንም ፡ በጽኑ ፡
ኃዘን ፡ አሳዘኑ ።
እነርሳቸው ፡ ሚስቶቻቸውና ፡ ልጆቻቸውን ፡ ፲፤
ከብቶቻቸውን ፡ ምንደኛው ፡ ስደተኛውን ፡ ሁሉ ፡
በዋጋም ፡ የገዙት ፡ ባሪያ ፡ ሰብስበው ፡ ማቅ ፡
ለብሰው ፡ አለቀሱ ።
ሚስቶቻቸውና ፡ የእስራኤል ፡ ወገኖች ፡ ሁሉ ፡ ፲፩፤
በኢየሩሳሌም ፡ የሚኖሩ ፡ ልጆቻቸውም ፡ በቤተ ፡
መቅደስ ፡ ደጃፍ ፡ ወደቁ ፡ በራሳቸውም ፡ ትቢያ ፡
ነሰነሱ ፡ በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ ማቃቸውን ፡
አነጠፉ ፡ መሠዊያውንም ፡ ማቅ ፡ አለበሱ ።
ልጆቻቸውን ፡ እንዳይነጥቁ ፡ ሚስቶቻቸውም ፡ ፲፪፤
እንዳይማረኩ ፡ ርስታቸው ፡ የሚሆኑ ፡ አገሮቻ
ቸውም ፡ እንዳይጠፉ ፡ መቅደሳቸውንም ፡ እን
ዳያሰድፉ ፡ ለአሕዛብም ፡ መዘበቻ ፡ እንዳያደር
ጉት ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ፈጣሪ ፡ አንድነት ፡ ፈጽ
መው ፡ ጮሁ ።
እግዚአብሔርም ፡ መከራቸውን ፡ አይቶ ፡ ልመ ፲፫፤
ናቸውን ፡ ሰማ ፡ ሕዝቡም ፡ በኢየሩሳሌምና ፡
በይሁዳ ፡ ሁሉን ፡ በሚገዛ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ማደሪያ ፡ በቤተ ፡ መቅደስ ፡ ብዙ ፡ ቀን ፡ ጾሙ ።
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ የሚቆሙ ፡ ካህናቱና ፡ ፲፬፤
ከፍ ፡ ያለ ፡ ካህን ፡ ኢዮአቄም ፡ የእግዚአብሔር
ንም ፡ ሥራ ፡ የሚሠሩ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ በወገባ
ቸው ፡ ማቅ ፡ ታጠቁ ፡ የዘወትሩን ፡ መሥዋዕት ፡
ሕዝቡ ፡ በፈቃድ ፡ የሚሠዉትንና ፡ የዕለቱን ፡
መሥዋዕት ፡ አገቡ ።
በራሳቸው ፡ አመድ ፡ ነሰነሱ ፡ በፍጹም ፡ ልቡና ፲፭፤
ቸውም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮሁ ፡ የእስራኤል
ንም ፡ ወገን ፡ በዓይነ ፡ ምሕረት ፡ ተመልከት ፡ አሉ ።

ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ለሰልፍ ፡ ተዘጋጁ ፡ የከ
ረብታቸውንም ፡ በሮች ፡ ዘጉ ። ያምባውንም ፡
ራሶች ፡ አጠሩ ፡ መንገዱንም ፡ ጕዳጕዕ ፡ አደ
ረጉ ፡ ብለው ፡ ለናቡከደነፆር ፡ ቢትወደድ ፡ ለሆ
ሎፎርኒስ ፡ ነገሩት ።
፪ እርሱም ፡ ፈጽሞ ፡ ተቈጣ ፡ የአሞንን ፡ ሹማም
ንትና ፡ የሞዓብን ፡ አለቆች ፡ የጳራልያንም ፡ አለ
ቆች ፡ ጠራቸው ።
፫ የከነዓን ፡ ልጆች ፡ በአምባ ፡ የሚኖሩ ፡ እሊህ ፡
ወገኖች ፡ ምንድናቸው ፡ በከረብታ ፡ የሚኖሩ ፡
ሠራዊታቸውም ፡ ብዙ ፡ የሆኑ ፡ እኒያስ ፡ ወገ
ኖች ፡ ምንድናቸው ፡ ጽናታቸውስ ፡ ምንድነው ፡
ከነርሳቸውስ ፡ የነገሠ ፡ ንጉሥ ፡ ማነው ። ወይስ ፡
ሹማቸው ፡ ወይስ ፡ አለቃቸው ፡ ማነው ።
፬ በምዕራብ ፡ ከሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ ይቀ
በሉኝ ፡ ዘንድ ፡ እንዴት ፡ አልመጡ ፡ ንገሩኝ ፡
አላቸው ።
፭ የአሞን ፡ ልጆች ፡ ሹም ፡ አክዮር ፡ ከኔ ፡ ከባር
ያህ ፡ እንደበት ፡ ይኸንን ፡ ነገር ፡ ስማ ፡ ከኔ ፡ ከባ
ርያህ ፡ አንደበት ፡ ሐሰት ፡ ነገር ፡ አይወጣምና ፡
በነዚህ ፡ አምባዎች ፡ በአቅራቢያህም ፡ ስለሚኖሩ ፡
ስለነዚህ ፡ ወገኖች ፡ እውነት ፡ ነገርን ፡ እነግርሃ
ለሁ ።
፮ እኒህ ፡ ወገኖች ፡ ከከላውዴዎን ፡ መጡ ።
፯ በከላውዴዎን ፡ አገር ፡ የሚኖሩ ፡ ያባቶቻቸውን ፡
ጣዖቶች ፡ ያመልኩ ፡ ዘንድ ፡ አልወደዱምና ።
፰ የወገኖቻቸውንም ፡ ሥርዓት ፡ ትተዋልና ፡ ላወ
ቁት ፡ ከጣዖቶቻቸው ፡ አንዛዝም ፡ ላወጣቸው ፡
ለሰማይ ፡ ፈጣሪ ፡ ለእግዚአብሔርም ፡ ሰግደዋ
ልና ፡ ቀድሞ ፡ በመስጴጦምያ ፡ ኖሩ ፡ ሸሽተው ፡
ወደ ፡ መስጴጦምያ ፡ ሔዱ ፡ በዚያም ፡ ብዙ ፡
ዘመን ፡ ኖሩ ።
፱ ፈጣሪያቸውም ፡ ከተሰደዱበት ፡ አገር ፡ ይወጡ ፡
ዘንድ ፡ አዘዛቸው ፡ ወደ ፡ ከነዓንም ፡ ሔደው ፡
በዚያ ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ ኖሩ ፡ ብርና ፡ ወርቅን ፡
ብዙ ፡ ከብቶችንም ፡ ፈጽመው ፡ አበዙ ።
፲ ረኃብ ፡ በከነዓን ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ ጸንቷልና ፡
ወደ ፡ ግብጽ ፡ ወረዱ ፡ መና ፡ እስኪመገቡ ፡
ድረስ ፡ በዚያ ፡ ኖሩ ፡ በዚያም ፡ በዙ ፡ መሉ ፡
ለወገኖቻቸውም ፡ ቍጥር ፡ የላቸውም ።
፲፩ የግብጽ ፡ ንጉሥም ፡ በጠላትነት ፡ ተነሣባቸው ፡
ተተነከለባቸው ፡ መከራም ፡ አጸናባቸው ፡ ጡብ ፡
በማሸከም ፡ ገዛቸው ፡ ባሮችንም ፡ አደረጋቸው ፡
፲፪ ወደ ፡ ፈጣሪያቸው ፡ ለመኑ ፡ እርሱም ፡ ድኅነት ፡
በሌለበት ፡ መቅሠፍት ፡ የግብጽ ፡ አገርን ፡ ሁሉ ፡
አጠፋ ፡ በፊታቸው ፡ ከግብጽ ፡ አገርም ፡ አወ
ጣቸው ።
፲፫ እግዚአብሔር ፡ በፊታቸው ፡ የኤርትራን ፡ ባሕር ፡
ከፍሎ ፡ አደረቃት ።
፲፬ በሲና ፡ ጐዳና ፡ ወደ ፡ ቃዴስ ፡ በርኔ ፡ ወሰዳቸው ፡
በአሞሬዎን ፡ የሚኖሩትንም ፡ ሁሉ ፡ አጠጣቸው ።
፲፭ በአሞራውያን ፡ አገርም ፡ ኖሩ ፡ ሐሴቦንንም ፡
ሁሉ ፡ በኃይሉ ፡ አጠፉ ፡ ዮርዳኖስንም ፡ ተሻግ
ረው ፡ አውራጃቸውን ፡ ሁሉ ፡ ወረሱ ።
፲፮ ከፌርዜዎንና ፡ ከከናኔዎን ፡ ከሴኬምና ፡ ከኢያ
ቡሴዎን ፡ ከጌርጌስዎንም ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ አወጣ
ቸው ፡ በዚያም ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ ኖሩ ።
፲፯ ፈጣሪያቸውን ፡ ባልበደሉ ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ በደ
ልን ፡ የሚጠላ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከነርሳቸው ፡
ጋራ ፡ በረድኤት ፡ አለና ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ከነ
ሳቸው ፡ ጋራ ፡ ጸንታ ፡ ኖረች ።
፲፰ ያዘዛቸውን ፡ ሥርዓት ፡ ባፈረሱ ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡
ፈጽሞ ፡ ብዙ ፡ በሆነ ፡ ጦር ፡ አጠፉቸው ፡ ተማ
ርከው ፡ ወደ ፡ ባዕድ ፡ አገር ፡ ሔዱ ፡ የፈጣሪያ
ቸው ፡ ማደሪያ ፡ ቤተ ፡ መቅደስም ፡ ፈረሰ ፡
ምድረ ፡ በዳም ፡ ሆነ ፡ አገሮቻቸውንም ፡ ጠላቶ
ቻቸው ፡ ያዙባቸው ።
፲፱ ዛሬ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ፈጣሪያቸው ፡ ተመለሱ ፡ ከተ
በተኑበትም ፡ አገር ፡ በዚያ ፡ ተሰበሰቡ ፡ ቤተ ፡
መቅደስ ፡ ባለበት ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ኖሩ ፡ ምድረ ፡
በዳ ፡ ነውና ፡ በተራራው ፡ ኖሩ ።
፳ አሁንም ፡ አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ እሊህ ፡ ወገኖች ፡
በደል ፡ እንዳለባቸው ፡ ፈጣሪያቸውንም ፡ የበ
ደሉት ፡ በደል ፡ ያለ ፡ እንደሆነ ፡ ይህ ፡ መሰናክ
ላቸው ፡ ነውና ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ እንጠይቅ ፡ ከዚያ ፡
በኋላ ፡ ወጥተን ፡ እንዋጋቸው ።
፳፩ በነዚህ ፡ ወገኖች ፡ በደል ፡ ከሌለባቸው ፡ ግን ፡
ጌታዬ ፡ አትደፋፈራቸው ፡ እነሆ ፡ ጌታቸው ፡
ፈጣሪያቸው ፡ ያጸናቸው ፡ ይሆናል ፡ ወይም ፡
ጠበቃ ፡ ሆኖ ፡ ይቆምላቸው ፡ ይሆናል ፡ ባገራ
ችን ፡ ሁሉ ፡ ኃፍረት ፡ እንሆናለን ፡ አለው ።
፳፪ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አክዮር ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ተናግሮ ፡
በጨረሰ ፡ ጊዜ ፡ በሰፈሩ ፡ ዙሪያ ፡ የቆሙ ፡ ወገ
ኖች ፡ ሁሉ ፡ አንጐራጐሩ ፡ ሹማምቱ ፡ በሞዓ
ብና ፡ በጳራልያ ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎችም ፡ ሁሉ ፡
ለሆሎፎርኒስ ፡ አክዮርን ፡ እንግደለው ፡ አሉት ።
፳፫ ከጽኑ ፡ አርበኛ ፡ ጋራ ፡ ይዋጉ ፡ ዘንድ ፡ ጽንና ፡
ኃይል ፡ የሌላቸው ፡ ወገኖች ፡ የእስራኤል ፡
ልጆችን ፡ የምንፈራቸው ፡ አይደለም ፡ አለ ።
፳፬ ነገር ፡ ግን ፡ ጌታችን ፡ ሆሎፎርኒስ ፡ ለጭፍራ
ዎችህ ፡ ሁሉ ፡ ምግብ ፡ ይሁን ።

ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በሸንጎው ፡ ዙሪያ ፡ ያሉ ፡ እነ
ዚያ ፡ ሰዎች ፡ ዝም ፡ ባሉ ፡ ጊዜ ፡ የናቡከደነፆር ፡
ቢትወደድ ፡ ሆሎፎርኒስ ፡ አክዮርን ፡ በሞዓብ ፡
ልጆች ፡ ሁሉና ፡ በኢሎፍሊ ፡ ወገኖች ፡ ፊት ።
፪ ዛሬ ፡ ትንቢት ፡ ትናገርልን ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ያጸናቸዋልና ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡
አትዋጓቸው ፡ ትለን ፡ ዘንድ ፡ ያሥሩ ፡ ነገድ ፡
ጠንቋይ ፡ አንተ ፡ ነህን ፡ ያለ ፡ ናቡከደነፆር ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ማነው ፡ አለው ።
፫ እርሱ ፡ መልክቱን ፡ ልኮ ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ፈጽሞ ፡
ያጠፋቸዋል ፡ ፈጣሪያቸው ፡ አያድናቸውም ፡
እኛም ፡ የናቡከደነፆር ፡ ባሮች ፡ እንደ ፡ አንድ ፡
ሰው ፡ እናጠፋቸዋለንና ፡ የፈረሶቻችንንም ፡

ኃይል ፡ አይቀዋወሙትም ።
፬ ተራሮቻቸውም ፡ በደማቸው ፡ ይሰክራሉ ፡ የል
ጆቻቸውም ፡ ሬሳ ፡ ይበዛል ፡ የዓለሙ ፡ ሁሉ ፡
ጌታ ፡ ንጉሡ ፡ ናቡከደነፆር ፡ አጠፋቸዋለሁ ፡
ብሏልና ፡ ቃሉ ፡ አሰት ፡ እንዳይሆን ፡ ከዚህ ፡
ዓለም ፡ ፈጽመው ፡ ይጠፋሉ ፡ እንጂ ፡ በፊታ
ችን ፡ በእግራቸው ፡ አይቆሙም ፡ አለ ።
፭ ዛሬ ፡ ይህንን ፡ ነገር ፡ የተናገርህ ፡ የአሞን ፡ ምን
ደኛ ፡ አክዮር ፡ አንተ ፡ ግን ፡ ከግብፅ ፡ አገር ፡
የወጡ ፡ እስራኤልን ፡ ተበቅዬ ፡ እስከጠፋቸው ፡
ድረስ ፡ በኃጢአትህ ፡ ከዚህ ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ እን
ግዴህ ፡ ወዲህ ፡ ፊቴን ፡ አታየውም ፡ አለው ።
፮ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ የወገኖቼና ፡ የጭፍራዎቼ ፡ ጦር ፡
ሰውነትህን ፡ ያጠፋል ፡ ሬሳህም ፡ ከሬሳቸው ፡
ጋራ ፡ ይወድቃል ።
፯ በተመለስሁም ፡ ጊዜ ፡ ባሮቼ ፡ ወደ ፡ አምባ
ቸው ፡ ይወስዱሃል ፡ ባቀበቱም ፡ካሉ ፡ አገሮቻ
ቸው ፡ በአንዲት ፡ አገር ፡ ያኖሩሃል ።
፰ እንዳችላቸው ፡ በልብህ ፡ ትታመናለህና ፡ እስ
ካጠፋቸውም ፡ ድረስ ፡ አይገድሉህም ፡ አለው ።
፱ እኔ ፡ ተናግሬአለሁና ፡ ከቃሌም ፡ የሚቀር ፡ የለ
ምና ፡ ሰውነትህ ፡ አትጠፋም ።
፲ ሆሎፎርኒስም ፡ በፊቱ ፡ በድንኳኑ ፡ ውስጥ ፡ የሚ
ቆሙ ፡ አሽከሮቹን ፡ አክዮርን ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡
ቤጤልዋ ፡ ይወስዱት ፡ ዘንድ ፡ እርሱንም ፡ ለእ
ስራኤል ፡ ልጆች ፡ ይሰጡቸው ፡ ዘንድ ፡ አዘዛ
ቸው ።
፲፩ አሽከሮቹም ፡ ይዘው ፡ ከሰፈሩ ፡ አደባባይ ፡ ወደ ፡
ምድረ ፡ በዳ ፡ ወሰዱት ፡ ከምድረ ፡ በዳውም ፡
መካከል ፡ ወደ ፡ ተራራው ፡ ሄዱ ፡ ከዚህም ፡
በኋላ ፡ በቤጤልዋ ፡ በታች ፡ ወዳሉ ፡ ምንጮች ፡
ደረሱ ።
፲፪ የዚያችም ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ባዩዋቸው ፡ ጊዜ ፡
መሣሪያቸውን ፡ ይዘው ፡ ከገር ፡ ወደ ፡ ተራ
ራው ፡ ራስ ፡ ሄዱ ። ምድር ፡ ነጐድ ፡ የያዙ ፡ ሰዎ
ችም ፡ ሁሉ ፡ ከኮረብታውን ፡ ጠበቁ ፡ በላያቸ
ውም ፡ መርግ ፡ ጣሉ ።
፲፫ የአክዮርንም ፡ እግር ፡ ብረት ፡ ፈቱት ፡ በተራ
ራውም ፡ በታች ፡ አሠሩት ፡ በዚያ ፡ በተራ
ራው ፡ በታች ፡ የወደቀ ፡ ሆኖ ፡ ትተውት ፡ ወደ ፡
ጌታቸው ፡ ተመለሱ ።
፲፬ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ከምባቸው ፡ ወርደው ፡
ወደሱ ፡ ሔዱ ፡ ፈትተውም ፡ ወደ ፡ ቤጤልዋ ፡
ወሰዱት ።
፲፭ አምባቸውን ፡ ለሚጠብቁ ፡ በዚያ ፡ ወራት ፡ ባሉ ፡
አለቆች ፡ ዘንድ ፡ አኖሩ ፡ እነዚሁም ፡ የጎቶንያ ፡
ልጅ ፡ ከብሪስና ፡ ከነገደ ፡ ስምዖን ፡ የተወለደ ፡
የሚካ ፡ ልጅ ፡ አገዛስ ፡ ናቸው ።
፲፮ በገራቸው ፡ ያሉ ፡ አለቆችን ፡ ሁሉ ፡ ጠሩ ፡ ሴቶ
ቻቸውና ፡ ጐልማሶቻቸው ፡ ሁሉ ፡ ሮጠው ፡
ወደ ፡ ሸንጎቻቸው ፡ ሔዱ ፡ አክዮርንም ፡ በሁሉ ፡
መካከል ፡ አቆሙት ፡ አገዛስም ፡ የተደረገውን ፡
ሁሉ ፡ ጠየቀው ።
፲፯ እንደ ፡ ተሰበሰቡ ፡ በናቡከደነፆር ፡ አሽከሮች ፡
አለቆች ፡ መካከልም ፡ ነገራቸውን ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡
ተናገሩ ፡ ሆሎፎርኒስም ፡ በእስራኤል ፡ ወገኖች ፡
ላይ ፡ እንደበቱን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ እንዳደረገ ፡ መልሶ ፡
የሆሎፎርኒስን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ነገራቸው ።
ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ በግምባራቸው ፡ ወድቀው ፡ ፲፰
ለእግዚአብሔር ፡ሰገዱ ፡ለመኑ ።
ሰማይን ፡ የፈጠርህ ፡ ፈጣሪ ፡ አቤቱ ፡ ትዕቢታቻ ፲፱
ውን ፡ ተመልክት ፡ የወገኖቻችንንም ፡ መከራ ፡
አይተህ ፡ ይቅር ፡ በል ። ማደሪያህ ፡ ቤት ፡ መቅ
ደስንም ፡ በዚች ፡ ቀን ፡ በዓይነ ፡ ምሕረት ፡ ተመ
ልከት ፡ ብለው ፡ ጮሁ ።
አክዮርንም ፡ ደስ ፡ አሰኙት ፡ ፈጽመውም ፡ አከ ፳
በሩት ።
አገዛስም ፡ ከተሰበሰቡበት ፡ ወስዶ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ፳፩
አገባው ፡ ለአለቆችም ፡ በዓልን ፡ አደረገ ፡ ይረ
ዳቸው ፡ ዘንድ ፡ የእስራኤልን ፡ ፈጣሪ ፡ በዚያች ፡
ሌሊት ፡ ሁሉ ፡ ለመኑት ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

ሆሎፎርኒስም ፡ ወደ ፡ ቤጤልዋ ፡ ይጓዙ ፡ ፩
ዘንድ ፡ ቀድመውም ፡ ወደ ፡ ተራራው ፡ ይሔዱ ፡
ዘንድ ፡ የእስራኤልንም ፡ ልጆች ፡ ይዋጓቸው ፡
ዘንድ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ የተሰለፉ ፡ ወገኖችና ፡ ጭፍ
ሮቹን ፡ ሁሉ ፡ በማግሥቱ ፡ አዘዛቸው ።
በዚያም ፡ ቀን ፡ የጸኑ ፡ አርበኞች ፡ የሆኑ ፡ ኃይ ፪
ለኞች ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ወረዱ ፡ እነዚያም ፡ ጓዝ ፡
ከሚጠብቁ ፡ ከልከበቡ ፡ ከብዙ ፡ አርበኞች ፡
ሰዎች ፡ በቀር ፡ አሥራ ፡ ሰባት ፡ እልፍ ፡ እግ
ረኞች ፡ እልፍ ፡ ከሁለት ፡ ሺህ ፡ ፈረሰኞች ፡
ናቸው ።
በቤጤሌዋ ፡ አጠገብ ፡ ባለች ፡ በአውሎንያ ፡ ፫
በወሀው ፡ ምንጭ ፡ ዘንድ ፡ ሰፈሩ ፡ የሰፈራቸ
ውም ፡ አቆልቋዩ ፡ እስከ ፡ ቤጤልምና ፡ እስከ ፡
ዶታይም ፡ ድረስ ፡ ወርዱም ፡ በአሴዴሬም ፡ አን
ፃር ፡ ካለ ፡ ከቤጤሌዋ ፡ እስከ ፡ ቅያስም ፡ ድረስ ፡
ደረሰ ።
የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ብዛታቸውን ፡ በዩ ፡ ፬
ጊዜ ፡ ፈጽመው ፡ደነገጡ ፡ እርስ ፡ በርሳቸውም ፡
እሊህ ፡ ሰዎች ፡ ዛሬ ፡ ምድርን ፡ ሁሉ ፡ ይሸፍኗ
ታል ፡ ደጋም ፡ ቢሆን ፡ ቆላም ፡ ቢሆን ፡ ብዛታ
ቸውንም ፡ የሚችል ፡ የለም ፡ ተባባሉ ።
ሁሉም ፡ መሣሪያቸውን ፡ ያዙ ፡ በምባቸውም ፡ ፭
እሳት ፡ አነደዱ ፡ በዚያች ፡ ሌሊት ፡ ሁሉ ፡ ሲጠ
ብቁ ፡ አደሩ ።
በሁለተኛውም ፡ ቀን ፡ ሆሎፎርኒስ ፡ በቤጤ ፮
ሌዋ ፡ ባሉ ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ፊት ፡ ፈረ
ሰቹን ፡ ጫነ ።
ያምባቸውን ፡ ኮረብታ ፡ ያዩ ፡ ዘንድ ፡ የውኃቻ ፯
ውን ፡ ምንጭ ፡ ይከቡ ፡ ዘንድ ፡ ወደዚያም ፡ እንዳይ
ደርሱ ፡ ይቀድሟቸው ፡ ዘንድ ፡ አርበኞች ፡ ሰዎ
ችም ፡ ይከቡ ፡ ዘንድ ፡ ጉበኞችን ፡ ላከ ።
እርሱም ፡ ከሠራዊቱ ፡ ጋራ ፡ ፈጥኖ ፡ ሔደ ፡ ፰
አርበኞች ፡ የሆኑ ፡ የኤሳው ፡ ልጆች ፡ አለቆ
ችም ፡ ሁሉ ፡ የጰራልያ ፡ መኳንንትና ፡ የሞዓብ ፡

ወገኖች ፡ ሹማምት ፡ ሁሉ ፡ ወደሱ ፡ መጡ ።
፱ በሚኖሩበቻው ፡ በከረብቶቻቸውና ፡ ባምባም
ቻቸው ፡ ነው ፡ እንጂ ።
፲ እነዚህ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ወገኖች ፡ የሚ
ታመኑ ፡ በጦራቸው ፡ አይደለምና ፡ በሥራዊትህ ፡
ጥፋት ፡ እንዳይደረግ ፡ አቤቱ ፡ ቃላችንን ፡ ስማ ፡
እሉት ፡ ላምባቸውም ፡ መውጫ ፡ የላቸውምና ።
፲፩ አቤቱ ፡ አሁንም ፡ በሰልፍ ፡ ሥርዓት ፡ አትዋጋ
ቸው ፡ ከሥራዊትህም ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ስንኳ ፡
የሚሞት ፡ የለም ።
፲፪ ነገር ፡ ግን ፡ ከሥራዊትህ ፡ ጋራ ፡ ጠብቃቸው ፡
በቤጤሉዋ ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ብዙ ፡
ውኃ ፡ ይቀዳሉና ፡ አሽከሮችህና ፡ የሥራዊትህ ፡
አርበኞች ፡ ሁሉ ፡ ከተራራው ፡ በታች ፡ የሚ
ፈልቅ ፡ የውኃቸውን ፡ ምንጮች ፡ ሁሉ ፡ እጽ
ንተው ፡ ይጠብቁ ።
፲፫ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ውኃ ፡ ጥም ፡ ይገድላቸዋል ፡
አገራቸውንም ፡ ላንተ ፡ ያስገዛሉ ፡ ሥራዊቶቻ
ችንና ፡ እኛም ፡ ላምባቸው ፡ ቅርብ ፡ ወደ ፡ ሆነ ፡
ቦታ ፡ ወደ ፡ ከረብታቸውም ፡ ራስ ፡ እንወጣለን ፡
ከምባቸው ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ስንኳ ፡ የሚወጣ ፡
እንዳይኖር ፡ በዚያ ፡ ሰፍረን ፡ እንጠብቃቸዋለን ።
፲፬ ሳይዋጓቸው ፡ እነርሳቸው ፡ ልጆቻቸውና ፡
ሚስቶቻቸውም ፡ በረኃብ ፡ ይጠፋሉ ፡ ባገራቸ
ውም ፡ ጐዳና ፡ ይወድቃሉ ።
፲፭ ከድተዋልና ፡ በፍቅርም ፡ አልተቀበሉህምና ፡
ጽኑ ፡ በቀልን ፡ ትበቀላቸዋለህ ፡ አሉት ።
፲፮ ቃላቸውም ፡ በሥራዊቱ ፡ ሁሉና ፡ በሆሎፎር
ኒስ ፡ ፊት ፡ ደስ ፡ አሰኘ ፡ እንደ ፡ ተናገሩም ፡
ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ።
፲፯ የአሞን ፡ ልጆች ፡ ሥራዊትም ፡ ተጓዙ ፡ አምስት ፡
ሺህ ፡ የሚሆኑ ፡ የናቡከደነፆርም ፡ አሽከሮች ፡
ከነርሳቸው ፡ ጋራ ፡ ነበሩ ፡ በአውሎኒም ፡ ሰፈሩ ፡
የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ምንጫቸውንና ፡ ውኃ
ቸውንም ፡ አስቀድመው ፡ ጠበቁ ።
፲፰ የአሞንና ፡ የኤሳውም ፡ ልጆች ፡ ወጥተው ፡ በዶ
ታይም ፡ አንጻር ፡ ባሉ ፡ ተራሮች ፡ ሰፈሩ ፡ ከነር
ሳቸውም ፡ በምኩር ፡ ወንዝ ፡ ባለ ፡ በኩሲ ፡
አጠገብ ፡ በኩል ፡ ባለ ፡ በኤቅሬቢን ፡ አንፃር ፡
ወዳለ ፡ ወደ ፡ ኤጴልዮጤንና ፡ በግራ ፡ በኩል ፡
ወዳሉ ፡ ወደ ፡ ምዕራብ ፡ ሰዎችን ፡ ላኩ ። የቀ
ሩቱ ፡ የፋርስ ፡ ሥራዊቶች ፡ ግን ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡
ሰፈሩ ፡ በገሩም ፡ ሁሉ ፡ አደሩ ፡ ከዚህም ፡ በኋላ ፡
ኳዛቸውን ፡ ከነርሳቸውም ፡ የሚበዛ ፡ የሌላ ፡
ሥራዊታቸውንና ፡ ብዙ ፡ ገንዘባቸውን ፡ አጓዙ ።
፲፱ ጠላቶቻቸው ፡ ስለ ፡ ከበቧቸው ፡ ከመካከላቸ
ውም ፡ መውጫ ፡ ስለሌላቸው ፡ ሰውነታቸው ፡
አእምሮዋን ፡ አጥታለችና ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡
ወደ ፡ ፈጣሪያቸው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮሁ ።
፳ የናቡከደነፆር ፡ አሽከሮች ፡ ከሥራዊቶቻቸው ፡
ሁሉ ፡ ጋራ ፡ አርበኞቻቸውም ፡ በፈረሶችና ፡ በሥ
ረገላ ፡ የተቀመጡ ፡ ሰዎች ፡ ከበዋቸው ፡ ሰባት ፡
ቀን ፡ ተቀመጡ ፡ በቤጤልዋ ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎ
ችም ፡ በቃቸው ፡ ያለ ፡ ውኃቸው ፡ ሁሉ ፡ አለቀ ።

የሚጠጡት ፡ ላንድ ፡ ቀን ፡ የሚያጠግባቸው ፡ ፳፩
ውኃ ፡ የላቸውም ፡ በመስፈሪያ ፡ ወደ ፡ መጠጣ
ትም ፡ ተመለሱ ።
ሚስቶቻቸውና ፡ ልጆቻቸው ፡ ጐልማሶቻቸ ፳፪
ውም ፡ ተጨነቁ ፡ በውኃ ፡ ጥም ፡ አለቁ ፡ በገር ፡
አደባባይ ፡ በበሩም ፡ ጐዳና ፡ ይወድቃሉ ፡ ከዚህ ፡
በኋላ ፡ ኃይል ፡ የላቸውም ።
ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ዖዝያን ፡ ተሰበሰቡ ፡ ጐል ፳፫
ማሶችና ፡ ያገር ፡ አለቆችም ፡ ልጆችና ፡ ሴቶ
ችም ፡ ተሰብስበው ፡ ወደ ፡ ዖዝያን ፡ ሔደው ፡
ቃላቸውን ፡ አሰምተው ፡ ጮሁ ።
ባለቆቻቸውም ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ በኛ ፡ ታላቅ ፡ ግፍ ፡ ፳፬
ታደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ከናቡከደነፆር ፡ አሽከሮች ፡
ጋራ ፡ በፍቅር ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ ባልተናገራችሁ ፡
በናንተና ፡ በኛ ፡ መካከል ፡ እግዚአብሔር ፡ ይፍ
ረድ ።
አሁንም ፡ የሚረዳን ፡ አጥተን ፡ በፊታቸው ፡ ፳፭
በውኃ ፡ ጥም ፡ በጽኑ ፡ ጥፋት ፡ እንጠፋ ፡ ዘንድ ፡
እግዚአብሔር ፡ በእጃቸው ፡ ጣለን ፡ አሉ ።
አሁንም ፡ ተገዙላቸው ፡ አገራችሁንም ፡ ሁሉ ፡ ፳፮
አስገዙላቸው ፡ ይበረብሩን ፡ ዘንድ ፡ እንገዛላቸ
ውም ፡ ዘንድ ፡ ሰውነታችን ፡ ትድን ፡ ዘንድ ።
የልጆቻችንን ፡ ሞት ፡ በይኖቻችን ፡ እንዳናይ ፡ ፳፯
ይሻለናልና ፡ የሆሎፎርኒስ ፡ ወገኖች ፡ ሥራዊ
ቱም ፡ ሁሉን ፡ ይበርብሩ ፡ የልጆቻችንና ፡ የሚ
ስቶቻችን ፡ ሰውነት ፡ አልቃለችና ።
እነሆ ፡ ምድርና ፡ ሰማይን ፡ እናሰማባችኋለን ፡ ፳፰
በዚች ፡ ቀን ፡ ዛሬ ፡ ይኸንን ፡ ነገር ፡ እንዳታደ
ርጉ ፡ እንዳባቶቻችን ፡ ኃጢአትና ፡ እንደ ፡
ኃጢአታችን ፡ የሚፈርድብን ፡ ፈጣሪያችን ፡
ያባቶቻችንም ፡ ፈጣሪ ፡ ነው ።
በወገኖቻቸው ፡ መካከል ፡ ጽኑ ፡ ልቅሶ ፡ ተደ ፳፱
ረገ ፡ ሁሉም ፡ አንድነት ፡ አለቀሱ ፡ ቃላቸው
ንም ፡ አሰምተው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮሁ ።
ዖዝያንም ፡ ሁለጊዜ ፡ በመከራው ፡ የሚጥለን ፡ ፴
አይደለምና ፡ ፈጣሪያችን ፡ እግዚአብሔር ፡ ቸር
ነቱን ፡ እስኪመልስልን ፡ ድረስ ፡ ወንድሞቻችን ፡
እመኑ ፡ ዳግመኛም ፡ አምስት ፡ ቀን ፡ መከራውን ፡
ታገሡ ።
እነዚህ ፡ አምስት ፡ ቀኖች ፡ ካለፉ ፡ በኋላ ፡ ረድ ፴፩
ኤቱን ፡ ካላደረገልን ፡ እንደ ፡ ተናገራችሁት ፡
እናደርጋለን ፡ አላቸው ።
ወንድሞቹንም ፡ በከተማ ፡ ባገራቸው ፡ ግምብና ፡ ፴፪
በአምባው ፡ ላይ ፡ በተናቸው ፡ ሄደውም ፡ ልጆ
ቻቸውንና ፡ ሚስቶቻቸውን ፡ አሰናበቱ ፡ እነር
ሳቸውም ፡ ፈጽመው ፡ ባገር ፡ የተጨነቁ ፡ ናቸው ።

ምዕራፍ ፡ ፰ ።

የሜራሪ ፡ ልጅ ፡ ዮዲት ፡ በዚያ ፡ ወራት ፡ ፩
ሰማች ፡ ይኸም ፡ ሜራሪ ፡ የዮክዮስ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡
ዮክዮስ ፡ የዮሴፍ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ ዮሴፍም ፡ የዖ
ዝያን ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ ዖዝያን ፡ የሕልቅያ ፡ ልጅ ፡
ነው ፡ ሕልቅያም ፡ የአናንዩ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ አና
ንዩ ፡ የጋድዩን ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ ጋድዩንም ፡ የሕ

ልቅዩ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ ሕልቅዩ ፡ የሬዎን ፡ ልጅ ፡
ነው ፡ ሬዎን ፡ የሐቂቆ ፡ ልጅ ፡ ሐቂቆም ፡ የኤል
ያስ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ ኤልያስም ፡ የኤልያብ ፡ ልጅ ፡
ነው ፡ ኤልያብ ፡ የናትናኤል ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ ናት
ናኤል ፡ የሰላምያል ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ ሰላምያል ፡
የሰላሰደዩ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ ሰላሰደዩም ፡ የእስራ
ኤል ፡ ልጅ ፡ ነው ።
፪ ባሏ ፡ ግን ፡ በገሯ ፡ ክለ ፡ ክወገኗ ፡ የተወለደ ፡
ምናሴ ፡ ይባል ፡ ነበር ፡ ነዶ ፡ ከሚያስሩ ፡ ሰዎች ፡
ጋራ ፡ በዱር ፡ ውሏልና ፡ የገብስ ፡ አዝመራ ፡ በደ
ረሰበት ፡ ወራት ፡ ሞተ ።
፫ ራሱን ፡ ምች ፡ መታው ፡ ታሞ ፡ ተኛ ፡ በገሩ ፡
በቤጤልዋ ፡ ሞቶ ፡ በገሩ ፡ እንዳባቶቹ ፡ በበላሞ
ንና ፡ በዶታይም ፡ ባለ ፡ በታ ፡ ቀበሩት ።
፬ ዮዲትም ፡ ከወንድ ፡ ተለይታ ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡
ከራት ፡ ወር ፡ በቤቷ ፡ ተቀመጠች ።
፭ በቤቷ ፡ ሰገነት ፡ ላይ ፡ የብሕትውና ፡ በታ ፡ አበ
ጀች ፡ በወገቧም ፡ ማቅ ፡ ታጠቀች ፡ የድኅነት ፡
ልብሷንም ፡ ለበሰች ።
፮ ከወንድ ፡ ተለይታ ፡ በኖረችበት ፡ ወራት ፡ ሁሉ ፡
ትጾም ፡ ነበረ ። ከቅዳሜና ፡ ከመበቻ ፡ ከበዓለ ፡
መጺለትና ፡ ከበዓለ ፡ ሰዊት ፡ ከበዓለ ፡ ፋሲካም ፡
በቀር ፡ አትበላም ፡ ነበር ።
፯ መልክ ፡ መልክም ፡ ፈጽማ ፡ እጅግ ፡ ደመ ፡ ግቡ ፡
ነበረች ፡ ምናሴም ፡ ብሩንና ፡ ወርቁን ፡ ሴቶችና ፡
ወንዶች ፡ አሽከሮችን ፡ ከብቶቹንም ፡ እርሻው
ንም ፡ ትቶላት ፡ ነበር ፡ በነርሳቸውም ፡ ሠልጥና ፡
ትኖር ፡ ነበር ።
፰ ፈጽማ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ትፈራ ፡ ነበርና ፡
በርሷ ፡ ክፉ ፡ ቃልን ፡ የሚናገር ፡ አልነበርም ።
፱ ውሀው ፡ ስላለቀ ፡ ሰውነታቸው ፡ አእምሮዋን ፡
አጥታለችና ፡ ሕዝቡ ፡ ባለቃቸው ፡ ላይ ፡ የተናገ
ሩት ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡ ሰማች ፡ ዮዲት ፡ ዖዝያን ፡
ለሕዝቡ ፡ የነገራቸውን ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ ከምስት ፡
ቀን ፡ በኋላም ፡ አገራቸውን ፡ ለፋርስ ፡ ሰዎች ፡
እንዲያስገዙ ፡ እንደ ፡ ማለላቸው ፡ ሰማች ።
፲ ልክ ፡ ገንዘቧን ፡ ሁሉ ፡ የምትጠብቅ ፡ ሞግዚ
ቷን ፡ ጠራቻት ፡ ከርሚኒና ፡ ክብርኒን ፡ ያገሩ
ንም ፡ አለቆች ፡ ጠራቻቸው ።
፲፩ ወደሷ ፡ መጡ ፡ ዛሬ ፡ በሕዝቡ ፡ ፊት ፡ የተናገራ
ችሁት ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ አይደለምና ፡ በቤጤሌዋ ፡
የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ሹማምቶች ፡ ስሙኝ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ በነዚህ ፡ ባምስቱ ፡ ቀኖች ፡ በይረዳ
ችሁ ፡ አገራችሁን ፡ ለጠላቶቻችሁ ፡ አሳልፋ
ችሁ ፡ ትሰጡ ፡ ዘንድ ፡ በእግዚአብሔርና ፡ በእ
ናንተ ፡ መካከል ፡ የተማማላችሁትን ፡ መሐላ ፡
በዚህ ፡ አጸናችሁ ።
፲፪ አሁን ፡ በዚህች ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔርን ፡ የምት
ፈታተኑት ፡ በሰውና ፡ በእግዚአብሔርም ፡ መካ
ከል ፡ የተነሣችሁ ፡ እናንተ ፡ ምንድናችሁ ።
፲፫ አሁንም ፡ እርሱ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይመረም
ራል ፡ እናንተ ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ሁለጊዜ ፡
የሚያደርገውን ፡ አታውቁም ።
፲፬ በሰው ፡ ልቡና ፡ ያለ ፡ ረቂቅ ፡ ምሥጢርን ፡ የማ
ታውቁ ፡ የልቡናውንም ፡ አሳብ ፡ የማታስተውሉ ፡
ይኸን ፡ ሁሉ ፡ ያደረገ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እን
ዴት ፡ ትመረመራላችሁ ፡ ልቡናውንስ ፡ መር
ምራችሁ ፡ ታውቁ ፡ ዘንድ ፡ እንዴት ፡ ትወዳላ
ችሁ ፡ ምክሩንስ ፡ መርምራችሁ ፡ ታገኙ ፡ ዘንድ ፡
እንዴት ፡ ትመረምራላችሁ ፡ ወንድሞቼ ፡ ለና
ንተ ፡ አገባብችሁ ፡ አይደለም ፡ ፈጣሪያችን ፡
እግዚአብሔርን ፡ አታሳዝኑት ።
በነዚህ ፡ ባምስቱ ፡ ቀኖች ፡ ይረዳን ፡ ዘንድ ፡ ፲፭
ቢወድም ፡ በወደደ ፡ ገንዘብ ፡ የሠለጠነ ፡ ነው ።
በዘመኑም ፡ ሁሉ ፡ ቢሆን ፡ በጠላቶቻችንም ፡
ፊት ፡ ያጠፉን ፡ ዘንድ ፡ ቢወድ ፡ የሠለጠነ ፡ ነው ።
እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ የሚጨክን ፡ አይ ፲፮
ደለምና ፡ እንደ ፡ ሰውም ፡ የሚቀየም ፡ አይደለ
ምና ፡ እናንተ ፡ ግን ፡ ፈጣሪያችሁ ፡ እግዚአብ
ሔርን ፡ አትፈታተኑት ።
ነገር ፡ ግን ፡ ከርሱ ፡ የምትገኝ ፡ ድኅነትን ፡ ደጅ ፡ ፲፯
ጥኑ ፡ ቃላችንን ፡ ሰምቶ ፡ ይረዳን ፡ ዘንድ ፡
ይወድ ፡ እንደሁ ፡ ለምኑት ።
በዘመናችን ፡ ጣዖት ፡ የሚያመልክ ፡ ሰው ፡ አል ፲፰
ተነሣምና ፡ ዛሬም ፡ ከኛ ፡ ወገንም ፡ ቢሆን ፡
ነገድም ፡ ቢሆን ፡ አገርም ፡ ቢሆን ፡ መንደርም ፡
ቢሆን ፡ ባባቶቻችን ፡ ዘመን ፡ እንደ ፡ ተደረገ ፡
ሰው ፡ ለሠራቸው ፡ ጣዖቶች ፡ የሚሰግዱ ፡ ሰዎች ፡
የሉምና ፡ ለምኑት ።
ስለዚህም ፡ ነገር ፡ አባቶቻችን ፡ ለመበርበርና ፡ ፲፱
ለጦር ፡ ሆኑ ፡ በጠላቶቻቸውም ፡ ፊት ፡ ጽኑ ፡
ጥፋትን ፡ ጠፉ ።
እኛ ፡ ግን ፡ ያለርሱ ፡ ሌላ ፡ ፈጣሪ ፡ አናውቅም ፡ ፳
ገንዘብ ፡ ባደረገን ፡ ጊዜ ፡ ሕጉን ፡ እንደ ፡ ጠበቅን ።
ይሁዳ ፡ ሁሉን ፡ እንደዚሁ ፡ አድርጓልና ፡ ከወገ ፳፩
ኖቻችን ፡ ቸል ፡ እንዳይለን ፡ በሱ ፡ እናምናለን ፡
ንዋየ ፡ ቅድሳታችን ፡ ጠፋ ፡ ባንደበታቸው ፡
በሚያመልኩት ፡ ጣዖታቸው ፡ ይመረምራቸ
ዋል ።
ወንድሞቻችን ፡ ጠፉ ፡ አገራችን ፡ ተዘረፈ ፡ የኛ ፡ ፳፪፳፫
ርስት ፡ ወደመሆን ፡ የሚመለስ ፡ ርስታችን ፡
ኢየሩሳሌምም ፡ ጠፋ ፡ በተገዘንላቸው ፡ መገዝ
ታችን ፡ ያለምስጋና ፡ ይሆናልና ፡ ፈጣሪያችን ፡
እግዚአብሔርም ፡ መዋረዳችንን ፡ አላየምና ፡
በሚገዙን ፡ ገንዘብ ፡ ባደረጉን ፡ በነዚያ ፡ በአሕ
ዛብ ፡ ዘንድ ፡ በመከራው ፡ የተሰነካከልን ፡ መገ
ዳደርያም ፡ እንሆናለን ።
እኛን ፡ ያዳምጣሉና ፡ ልቡናቸውም ፡ ወደኛ ፡ ፳፬
ተሰቅሏልና ፡ መሠዊያውና ፡ ቤተ ፡ መቅደስም ፡
በኛ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራልና ፡ ወንድሞቻችን ፡ አሁ
ንም ፡ ለባልንጀሮቻችን ፡ ንገሯቸው ።
አባቶቻችንን ፡ እንደፈተናቸው ፡ የሚፈታተን ፡ ፳፭
ፈጣሪያችን ፡ እግዚአብሔርን ፡ በዚህ ፡ ሁሉ ፡
እናመስግነው ።
ለአባቶቻችን ፡ ያደረገውን ፡ ሁሉ ፡ አብርሃምን ፡ ፳፮
እንደ ፡ ተፈታተነው ፡ ይስሐቅንም ፡ እንደ ፡
ተፈታተነው ፡ የናቱ ፡ አበት ፡ የላባን ፡ በጎች ፡
ሲጠብቅ ፡ የሶርያ ፡ ክፍል ፡ በምትሆን ፡ በመስ

ጺጠምዩ ፡ ያዕቆብንም ፡ እንደ ፡ ተፈታተነው ፡ አስቡ ፡፡
፳፯፤ እነሳቸውን ፡ በተፈታተናቸው ፡ ጊዜ ፡ ልቡና ቸውንም ፡ በመረመረ ፡ ጊዜ ፡ የሚቀርቡትን ፡ ሰዎች ፡ ይቀር ፡ ይላቸው ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያጠፋቸው ፡ አይደለምና ፡ እኛ ንም ፡ የበደለን ፡ አይደለምና ፡ አ ቡ ፡ አለች ፡፡
፳፰፤ ዖዝያንም ፡ የተናገርሽውን ፡ ሁሉ ፡ በበጎ ፡ ልቡና ፡ ተናገርሽ ፡ የልቡናሽ ፡ ተፈጥሮ ፡ ደግ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡፡
፳፱፤ ከመጀመርያው ፡ ዘመንሽ ፡ ጀምሮ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በጥበብሽ ፡ አወቀሽ ፡ እንጂ ፡ ጥበብሽ ፡ ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ የተሰማ ፡ አይደለምና ፡ ቃልሽንም ፡ የሚነቅፈው ፡ የለም ፡፡
፴፤ ነገር ፡ ግን ፡ ሕዝቡ ፡ ፈጽመው ፡ ተጠምተዋልና ፡ እንዳሉን ፡ እናደርግ ፡ ዘንድ ፡ ዘበዘቡን ፡ መሓላ ፡ የማይቻለን ፡ መሐላንም ፡ አመጡብን ፡፡
፴፩፤ አንቺ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የምትፈሪ ፡ ሴት ፡ ነሽና ፡ እግዚአብሔር ፡ ዝናምን ፡ ያዘንምልን ፡ ዘንድ ፡ ኩሬያችንም ፡ ይመላ ፡ ዘንድ ፡ እንግዲህ ፡ ወዲህም ፡ እንዳንጠማ ፡ ለምኝልን ፡ አሏት ፡፡
፴፪፤ ዮዲትም ፡ ስሙኝ ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ዘመን ፡ የሚነገር ፡ ሥራን ፡ እሠራለሁ ፡ አለቻቸው ፡፡
፴፫፤ እናንተ ፡ ግን ፡ በዚች ፡ ሌሊት ፡ በበሩ ፡ ቁሙ ፡ እኔም ፡ ከብላቴናዬ ፡ ጋራ ፡ እወጣለሁ ፡ አገራችንን ፡ አሳልፈን ፡ ለጠላቶቻችን ፡ እንሰጣለን ፡ በምትሉበት ፡ በነዚያም ፡ ወራቶች ፡ የእስራኤል ፡ ፈጣሪ ፡ እግዚአብሔር ፡ ረድቶ ፡ በጄ ፡ ያድናል ፡፡
፴፬፤ እኔ ፡ የምሠራው ፡ ሥራ ፡ እስኪፈጸም ፡ ድረስ ፡ አልነግራችሁምና ፡ እናንተ ፡ ግን ፡ የምሠራውን ፡ ሥራ ፡ አትመርምሩኝ ፡ አለቻቸው ፡፡
፴፭፤ አለቆቻቸውና ፡ ዖዝያንም ፡ በፍቅር ፡ ሂጂ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ካንቺ ፡ ጋራ ፡ ይሂድ ፡ ባንቺም ፡ ሬት ፡ ጠላቶቻችንን ፡ ተበቅሎ ፡ ያጠፋል ፡ አሏት ፡፡
፴፮፤ ተመልሰው ፡ ወደ ፡ ባልንጀሮቻቸው ፡ ሄዱ ፡፡

ምዕራፍ ፡ ፱ ፡፡

፩፤ ዮዲት ፡ ግን ፡ በግምባሯ ፡ ተደፍታ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ወደቀች ፡ በራሷም ፡ ላይ ፡ ትቢያ ፡ ነሰነሰች ፡ የምትለብሰውንም ፡ ማቅ ፡ አሳየች ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ የተዘጋጀ ፡ ዕጣንን ፡ ቍርባን ፡ አድርጋ ፡ አገባች ፡፡
፪፤ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ዮዲት ፡ ቃሏን ፡ አሰምታ ፡ ጮኸች ፡ በማኅፀን ፡ ያለ ፡ ዕንስን ፡ ያጠፉ ፡ ድንግልንም ፡ ያጐሰቈሉ ፡ ልብስንም ፡ የገፈፉ ፡ በከተማ ፡ በራቱ ፡ ማዕዘን ፡ ማኅፀንንም ፡ ያሳደፉ ፡ ጠላቶችን ፡ ተበቅሎ ፡ ለማጥፋት ፡ ለስምዖን ፡ በጁ ፡ ጦር ፡ የሰጠኸው ፡ ያባቴ ፡ ፈጣሪ ፡ አቤቱ ፡ ልመናዬን ፡ ስማኝ ፡ ነገሩ ፡ እንዲህ ፡ አይደለም ፡ አለች ፡፡
፫፤ ሳለቆቻቸው ፡ በሰልፍ ፡ ጊዜ ፡ ኃይልን ፡ ሰጥተሃቸዋልና ፡ መኝታቸውም ፡ በሞቱ ፡ በሮች ፡ ደም ፡ ተነክሯልና ፡ እነርሱ ፡ ግን ፡ የወደዱትን ፡ አደረጉ ፡ ኃይለኞችንና ፡ አርበኞችንም ፡ ከዙፋናቸው ፡ እየገለበጥህ ፡ ጣልሃቸው ፡፡
ልጆቻቸውና ፡ ሚስቶቻቸውም ፡ ተማረኩ ፡ በንተ ፡ ዘንድ ፡ የተወደዱ ፡ ለአምላክነትህም ፡ የቀኑ ፡ የረከሰ ፡ ደማቸውንም ፡ የተጸየፉ ፡ ትረዳቸውም ፡ ዘንድ ፡ የለመኑ ፡ የልጆችን ፡ ምርኮ ፡ ሁሉ ፡ ተካፈሉ ፡፡ ፬፤
ከዚህ ፡ አስቀድሞ ፡ ለግብፃውያን ፡ ታምራት ፡ አድርገሃልና ፡ ፈጣሪዬ ፡ እግዚአብሔር ፡ እኔን ፡ ድኃይቱን ፡ ልመናዬን ፡ ስማኝ ፡ በነሰናክሬም ፡ በነብልጣሶር ፡ በነሆሎፎርኒስ ፡ በዕርጓውያንም ፡ የተደረገውን ፡ አንተ ፡ አውቀህ ፡ አንተም ፡ በወቅህ ፡ ገንዘብ ፡ ተደረገ ፡፡ ፭፤
ምክርህም ፡ የቀና ፡ ነው ፡ ሥርዓትህ ፡ የተዘጋጀ ፡ ነውና ፡ ፍርድህንም ፡ በወቅህ ፡ ገንዘብ ፡ ፈርደሃልና ፡ እነሆ ፡ በረድኤት ፡ መጣህ ፡ ይሉሃል ፡ እነሆ ፡ የፋርስ ፡ ሰዎች ፡ ከሠራዊታቸው ፡ ጋራ ፡ በዝተዋልና ፡ በፈረሶቻቸውም ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብለዋልና ፡ በፈረስም ፡ የተቀመጡ ፡ ሰዎች ፡ በኃይላቸው ፡ ታምነዋልና ፡ አርበኞችም ፡ በጽናታቸው ፡ በቀስታቸውና ፡ በጦራቸው ፡ በምድር ፡ ነገዳቸውም ፡ ታምነዋልና ፡ አንተ ፡ አርበኞችን ፡ የምታጠፋ ፡ ፈጣሪ ፡ እንደ ፡ ሆንክ ፡ አላወቁህምና ፡ ስምህም ፡ አሸናፊ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አላወቁምና ፡፡ ፮፤
አንተ ፡ ከሠራዊታቸው ፡ ጋራ ፡ በከሃሊነትህ ፡ አጠፋሃቸው ፡ ቤተ ፡ መቅደስን ፡ ያጐሰቍሉ ፡ ዘንድ ፡ የስምህ ፡ ጌትነት ፡ ማደሪያ ፡ የሆነች ፡ ደብተራ ፡ ኦሪትንም ፡ ያሳድፉ ፡ ዘንድ ፡ መክረዋልና ፡ በብረትም ፡ የመሠዊያህን ፡ ቀንዶች ፡ አፍርሰዋልና ፡ አርበኞቻቸውን ፡ ተቈጥተህ ፡ አጥፋቸው ፡፡ ፯፤
ትዕቢታቸውንም ፡ እይተህ ፡ በራሳቸው ፡ ቍጣህን ፡ አምጣ ፡ ባንደበቴ ፡ አታልዬ ፡ ሆሎፎርኒስን ፡ ንጉሡን ፡ ባለሟሉንም ፡ እገድል ፡ ዘንድ ፡ ባሰብኩ ፡ ገንዘብ ፡ በእኔ ፡ በድኃይቱ ፡ እጅ ፡ ኃይልን ፡ አድርግ ፡፡ ፰፤
ረድኤትህ ፡ ሉብዙ ፡ ሰዎች ፡ አይደለምና ፡ ኃይልህም ፡ ለአርበኞች ፡ አይደለምና ፡ ሰውነታቸውን ፡ በኔ ፡ በሴቲቱ ፡ እጅ ፡ አጥፋ ፡፡ ፱፤
ለጥቂቶች ፡ ሰዎች ፡ አንተ ፡ ረዳታቸው ፡ ነህና ፡ የደከሞችም ፡ ኃይላቸው ፡ ነህና ፡ በመከራ ፡ የጠፉ ፡ ሰዎችንም ፡ የምታድናቸው ፡ አንተ ፡ ነህና ፡ ተስፋ ፡ የቆረጡ ፡ ሰዎችንም ፡ የምታድናቸው ፡ አንተ ፡ ነህና ፡ አቤቱ ፡ አዋርዳቸው ፡ እንጂ ፡ አታክብራቸው ፡፡ ፲፤
ያባቶቼ ፡ ፈጣሪ ፡ የእስራኤልም ፡ ያባቶቻቸው ፡ ፈጣሪ ፡ ምድርና ፡ ሰማዩን ፡ ውሀንም ፡ የፈጠርህ ፡ አቤቱ ፡ አዎን ፡ አንተ ፡ ነህኮ ፡ የፍጥረትህ ፡ ሁሉ ፡ ገዥ ፡ አንተ ፡ ነህ ፡ አንተ ፡ ልመናዬን ፡ ስማ ፡፡ ፲፩፤
ያስታቸው ፡ ዘንድ ፡ ያሳዝናቸው ፡ ዘንድ ፡ የማ ፲፪፤

ደርያህ ፡ የቤት ፡ መቅደስና ፡ የሕግህ ፡ የጽዮን
ንም ፡ ሥርዓት ፡ ድንቅ ፡ ነገርን ፡ የመከሩ ፡ የል
ጆችህ ፡ ያነዋወራቸው ፡ ጠላቶች ፡ ያጠፉቸው ፡
ዘንድ ፡ ቃሌን ፡ እንዲያጠፉቸው ፡ አድርግ ።
፲፬ የአርበኛውና ፡ የኃይለኛው ፡ ሁሉ ፡ ገዥ ፡ አንተ ፡
እግዚአብሔር ፡ እንደሆንክ ፡ የእስራኤልንም ፡
ወገን ፡ ካንተ ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ የሚያጸናቸው ፡ እን
ደሌለ ፡ ያውቁ ፡ ይረዱ ፡ ዘንድ ፡ ለሕዝቡ ፡ ለአ
ሕዛቡ ፡ ሁሉ ፡ እንዲያውቁ ፡ አድርግ ፡ አለች ።

ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ፈጣሪ ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለምና ፡ በጨረሰች ፡ ጊዜ ፡
ይህን ፡ ሁሉ ፡ ነገር ፡ ጨርሳ ፡ ከወደቀችበት ፡
በታ ፡ ተነሣች ።
፪ ብላቴናዋንም ፡ ጠርታ ፡ ቀዳሚ ፡ ቀዳሚን ፡
በምታከብርበት ፡ በዓልንም ፡ በምታደርግበት ፡
ወራት ፡ ወደምትቀመጥበት ፡ ቤቷ ፡ ወረደች ።
፫ የለበሰችውን ፡ ማቅ ፡ አወለቀች ፡ የድኅነቷን ፡
ልብስ ፡ ለበሰች ፡ ሰውነቷንም ፡ በውኃ ፡ ታጠ
በች ፡ ሽቱን ፡ ተቀባች ፡ ራሷንም ፡ ተሠራች ፡
አጌጠች ፡ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ባሏ ፡ ምናሴ ፡ በሕ
ይወት ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ የምትለብሰው ፡ የተድላዋ ፡
የደስታ ፡ ልብሷን ፡ ለበሰች ።
፬ ጫማዋንም ፡ ተጫማች ፡ ዝርግፉን ፡ ቀለበቷ
ንና ፡ አምባርዋን ፡ ንሮዋን ፡ ጌጡንም ፡ ሁሉ ፡
አጌጠች ፡ የሚያይዋትን ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ዓይን ፡
እስክታስት ፡ ድረስ ፡ ፈጽማ ፡ አጌጠች ።
፭ ወይን ፡ ያለበትን ፡ ገምቦ ፡ ዘይት ፡ ያለበትን ፡
ማሰሮ ፡ ትሸከም ፡ ዘንድ ፡ ለብላቴናዋ ፡ ሰጠ
ቻት ፡ ስልቅ ፡ በሶን ፡ የስንዴ ፡ አምባሻና ፡ በለስ
ንም ፡ በዕቃዋ ፡ መላች ፡ ገንዘቧን ፡ ሁሉ ፡ አን
ግታ ፡ አሸክማ ፡ ወደ ፡ ቤጤሌዋ ፡ ሔደች ።
፮ ያገር ፡ አለቆችንና ፡ ያዝያንን ፡ ከርሚንና ፡ ከብ
ሪምንም ፡ በዚያ ፡ ቆመው ፡ አገኘቻቸው ።
፯ ፊቷ ፡ ተለውጦ ፡ የምታስደንቅ ፡ እንደሆነች ፡
በይዋት ፡ ጊዜ ፡ ልብሷን ፡ ለብሳ ፡ በይዋት ፡
ጊዜ ፡ ከደምግባቷ ፡ ማማር ፡ የተነሣ ፡ ፈጽመው ፡
እጅግ ፡ ተደነቁ ።
፰ ኢየሩሳሌምንና ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ለማ
ጽናት ፡ በልብሽ ፡ ያሰብሽውን ፡ ታደርጊ ፡ ዘንድ ፡
የእስራኤል ፡ ፈጣሪ ፡ መወደድን ፡ ይስጥሽ ፡
አሏት ፡ እርሷም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሰገደች ።
፱ አሁንም ፡ ከናንተ ፡ ጋራ ፡ የተናገርሁትን ፡ ነገር ፡
ወጥቼ ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ ያምባውን ፡ በር ፡ የሚ
ከፍትልኝ ፡ ሰው ፡ እዘዙልኝ ፡ አለቻቸው ፡ እንደ ፡
ተናገረች ፡ ይከፍቱላት ፡ ዘንድ ፡ ጐልማሶችን ፡
አዘዙአቸው ።
፲ እንደዚሁ ፡ አደረጉ ፡ ዮዲት ፡ ወጣች ፡ ብላቴና
ዋም ፡ ከርሷ ፡ ጋራ ፡ ወጣች ፡ ከምባው ፡ ወርዳ ፡
ወደ ፡ አውሎኒ ፡ እስክትሔድም ፡ ድረስ ፡ ያገሩ ፡
ሰዎች ፡ ያይዋት ፡ ነበር ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡
አላይዋትም ።
፲፩ አቅንታ ፡ ወደ ፡ አውሎኒ ፡ ሄደች ፡ የፋርስ ፡ ዘበ
ኞችም ፡ አገኟት ።
ይዘው ፡ መረመሯት ፡ አንቺ ፡ ማነሽ ፡ ወዴት ፡ ፲፪
ትሄጃለሽ ፡ ከየትስ ፡ መጣሽ ፡ አሏት ። እኔ ፡ ከዕ
ብራውያን ፡ የተወለድኩ ፡ ነኝ ፡ አገራቸውን ፡
ለናንተ ፡ አሳልፈው ፡ ሊሰጡ ፡ በወደዱ ፡ ጊዜ ፡
ከነርሳቸው ፡ ኰብልዬ ፡ መጣሁ ።
እኔ ፡ እውነተኛ ፡ ነገርን ፡ እነግረው ፡ ዘንድ ፡ የም ፲፫
ትሄዱበት ፡ ጐዳናንም ፡ አሳየው ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡
ቢትወደዳችሁ ፡ ወደ ፡ ሆሎፎርኒስ ፡ አስቀድሜ ፡
መጣሁ ፡ አውራጃቸውንም ፡ ሁሉ ፡ ገንዘብ ፡ ታደ
ርጋላችሁ ፡ ከሰዎቻችሁም ፡ አንድ ፡ ሰውስ ፡
ስንኳ ፡ የሚቈስል ፡ የለም ፡ አለቻቸው ።
እነዚያም ፡ ሰዎች ፡ ቃሏን ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ፊቷ ፲፬
ንም ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ፡ ደም ፡ ግባቷም ፡ በፊታቸው ፡
ፈጽሞ ፡ የተደነቀ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ባዩ ፡ ጊዜ ።
አሁንም ፡ ወደ ፡ ጌታችን ፡ ፈጥነሽ ፡ የወረድሽ ፡ ፲፭
አንቺ ፡ ሰውነትሽን ፡ አዳንሽ ። አሁንም ፡ ወደ ፡
ድንኳኑ ፡ ሂጂ ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ የሚያደርስሽን ፡
ሰው ፡ ከኛ ፡ እንልክለን ።
በፊቱም ፡ በቆምሽ ፡ ጊዜ ፡ ይኸንን ፡ ነገር ፡ ንገ ፲፮
ሪው ፡ እንጂ ፡ ልቡናሽ ፡ አይፍራ ፡ በጎ ፡ ነገርን ፡
ያደርግልሻል ፡ አሏት ።
ከነርሳቸው ፡ መቶ ፡ ሰው ፡ መረጡ ፡ የርሷን ፡ ነገር ፡ ፲፯
እስኪነግሩት ፡ ድርስ ፡ ደረሰው ፡ ከብላቴናዋ ፡
ጋራ ፡ ወስደው ፡ ወደ ፡ ሆሎፎርኒስ ፡ አደረሷት ።
ደም ፡ ግባቷን ፡ አደነቁ ፡ በእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ፲፰
ስለርሷ ፡ ተደነቁ ፡ እርስ ፡ በርሳቸውም ፡ እንዲህ ፡
ተባባሉ ፡ ከነርሳቸው ፡ አንድ ፡ ሰውን ፡ ያስቀሩ ፡
ዘንድ ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ አልሆነምና ፡ ከነርሳቸው ፡
እንደዚህ ፡ ያሉ ፡ ሴቶች ፡ ሳሉ ፡ እሊህን ፡ ወገ
ኖች ፡ ንቆ ፡ የሚተዋቸው ፡ ማነው ፡ ተባባሉ ፡
እነዚህስ ፡ እነአክዮር ፡ ተዋቸው ፡ የሚሉ ፡ በሰው ፡
ሁሉ ፡ ተተንኰለው ፡ ነው ፡ አሉ ።
በሆሎፎርኒስ ፡ ዘንድ ፡ የተቀመጡ ፡ አሽከሮ ፲፱
ቹም ፡ ሁሉ ፡ መጥተው ፡ ወደ ፡ ድንኳኑ ፡ አገ
ቧት ።
ሆሎፎርኒስም ፡ ዋጋው ፡ ብዙ ፡ በሆነ ፡ መረግድ ፡ ፳
በሚባል ፡ ዕንቍና ፡ በወርቅ ፡ የተለበጠ ፡ ነጭ ፡
ሐር ፡ ልብስ ፡ በተነጠፈበት ፡ በድንኳኑ ፡ ውስጥ ፡
ባለ ፡ በዙፋኑ ፡ ላይ ፡ ተኝቶ ፡ ነበረ ።
የርሷን ፡ ነገር ፡ ነገሩት ፡ ጉብጋቦ ፡ የሚባለው ፡ ፳፩
ብላቴናውም ፡ ወጣ ፡ በፊቱም ፡ የብር ፡ መቅረዝ ፡
ፋና ፡ ያበሩ ፡ ነበር ።
ዮዲትም ፡ ወደርሱ ፡ በመጣች ፡ ጊዜ ፡ አሽከሮቹ ፡ ፳፪
ቆመው ፡ ነበር ፡ ከመልኳ ፡ ከደም ፡ ግባቷ ፡ የተ
ነሣ ፡ ሁሉም ፡ ተደነቁ ፡ እርሷም ፡ በግምባሯ ፡
በምድር ፡ ላይ ፡ ወድቃ ፡ ሰገደችለት ፡ አሽከሮ
ቹም ፡ አነሥዋት ።

ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

ሆሎፎርኒስም ፡ አንቺ ፡ ሴት ፡ እመኚ ፡ ለዓ ፩
ለሙ ፡ ሁሉ ፡ ንጉሥ ፡ ለናቡከደነፆር ፡ ይገዛ ፡
ዘንድ ፡ ራሱን ፡ ወደርሱ ፡ በመለሰ ፡ ሰው ፡ እኔ ፡
ክፉ ፡ ነገር ፡ አላደርግምና ፡ ልቡናሽም ፡ አይፍ

ራብሽ ።
፪፤ አሁንም፡ከምብ፡የሚኖሩ፡አሊህ፡ወገኖችሽ፡
የወነጀሉኝ፡ባይሆኑ፡በነርሳቸው፡ጦሬን፡ባላ
ነሣሁም፡ነበር፡ይህን፡ነገር፡እነርሳቸው፡አደ
ረጉት፡እንጂ፡እኔ፡ያደረግሁት፡አይደለም ።
፫፤ አሁንም፡ንገሪኝ፡ከነርሳቸው፡ዘንድ፡ስለምን፡
ነገር ፡ ኰብለሽ ፡ ወደኔ ፡ መጣሽ፡ነገር ፡ ግን ፡
ለሕይወትሽ ፡ መጣሽ ፡ በዚች ፡ ቀን ፡ ከመከ
ራው፡እንድትድኚ፡እመኚ ።
፬፤ ለንጉሡ፡ለጌታችን፡ለናቡከደነፆር፡አሽከሮች፡
በጎ ፡ ነገር ፡ እንድናደርግ ፡ ላንቺ ፡ ከምንናገ
ረው፡ ከበጎ፡ነገር፡በቀር፡ባንቺ፡ክፉ፡ነገር፡
የሚያደርግ፡የለም፡አላት ።
፭፤ ዮዲትም ፡ የኔን ፡ የባርያህን ፡ ቃል ፡ ከሰማህ ፡
እኔ ፡ ባሪያህ፡ በፊትህ፡እነግርሃለሁ፡በዚች፡
ሌሊት፡እኔ፡ለጌታዬ፡ሐሰት፡ነገር፡አልናገ
ርህም ።
፮፤ የኔን ፡ የባሪያህን ፡ ቃል ፡ ከሰማህ፡እግዚአብ
ሔር ፡ ላንተ ፡ ፍጹም ፡ ሥራ ፡ ይሠራልሃል፡
ለዓለም ፡ ሁሉ ፡ የነገሡ፡ናቡከደነፆር፡በሕይ
ወት፡ይኖራልና፡ሰውን፡ሁሉ፡ታድን፡ዘንድ፡
የላከህ ፡ አንተም ፡ ቢትወደዱ ፡ በሕይወት ፡
ትኖራለህና ።
፯፤ አንተ ፡ ጌታዬ ፡ ከሰብከው፡ነገር፡የሚወጣ፡
የለም ፡ እንስሳና ፡ በምድረ ፡ በዳ፡የሚኖሩ፡
አውሬዎች ፡ በሰማይ ፡ የሚበሩ ፡ ወፎችም፡
ስለኀይልህ ፡ ስሠራዊቱና ፡ ላንተ ፡ ለናቡከደነ
ፆር፡ ተገዝተው፡በሕይወት፡ይኖራሉ፡እንጂ፡
በዘመንህ ፡ ሰዎች ፡ ብቻ ፡ የሚገዙልህ ፡ አይደ
ለም ።
፰፤ የልቡናህን፡ጥበብና፡ሥራህን ፡ ሰምተናልና፡
ከግዛቱ ፡ ሁሉ ፡ አንተ ፡ ብቻ ፡ ቸር ፡ እንደ
ሆንክ፡ባገሩም ፡ ሁሉ ፡ ተሰምቷልና ፡ በሥራ
ህም፡ሁሉ፡አንተ፡አርበኛ፡ነህና፡በሰልፍህም፡
ሁሉ፡አንተ፡የተደነቅህ፡ነህና፡ሰዎች፡ብቻ፡
የሚገዙልህ፡አይደለም ።
፱፤ አሁንም፡አክዮር፡በሰፈራችሁ፡የነገራችሁን፡
ነገር፡የቤጤሌዋ፡ሰዎችም፡አክዮርን፡አዳኑት፡
ብለው፡የነገሯችሁንም፡ነገር፡ሁሉ፡ሰማን ።
፲፤ ፈጣሪያቸውን ፡ ካልበደሉ ፡ ወገኖቼ፡እስራኤ
ልን፡ ተበቅሎ፡ማጥፋት፡የማይችል፡ስለሆነ፡
ጦርም ፡ እነርሳቸውን ፡ ማጥፋት ፡ የማይችል ፡
ስለሆነ ፡ ነገሩ ፡ እንደርሱ ፡ እውነት፡ነውና፡
በልብህ፡ኣኑረው፡እንጂ፡ጌታችን፡በልብህ፡
አትናቅ ።
፲፩፤ አሁንም ፡ ጌታዬ ፡ በማይረባ ፡ በማይጠቅም ፡
የተናቅህ ፡ እንዳትሆን ፡ በፊትህ ፡ ሞታቸው ፡
በሚደርስባቸው፡ገንዘብ፡በበደላቸው፡ሥራ፡
ፈጣሪያቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ባሳዘኑበት ፡
በዚህ፡ኀጢአታቸው፡ታገኛቸዋለህ ።
፲፪፤ እህላቸው ፡ አልቋልና ፡ ተሸክመው ፡ ወዳም
ባው፡ያገቡት፡ውኃቸውም፡አልቋልና፡ከብ
ታቸውንም፡ይበሉ፡ዘንድ፡ወደ፡መብላት፡
ተመልሰዋልና ፡ እንዳይበሉ ፡ ፈጣሪያቸው ፡
በኦሪት፡የከለከላቸውን፡ይኸን፡ይበሉ፡ዘንድ፡
ደርሰዋልና ።
የወይናቸውን፡አሥራትና፡የእህላቸውን፡መጀ ፲፫፤
መሪያ፡ በፈጣሪያችን ፡ ፊት ፡ በኢየሩሳሌም ፡
ለሚቆሙ ፡ ለክህናት ፡ የለዩትን ፡ ከሕዝቡም ፡
ላንድ ፡ ሰው ፡ ስንኳ ፡ በእጃቸው ፡ መዳሰስ፡የማ
ይገባቸውን፡ይኸንን፡በይቱንም፡ሊበሉ፡አስ
በዋልና ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ ልከዋልና ፡
በዚህ፡ታገኛቸዋለህ ።
በዚያ፡በኢየሩሳሌም ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ እን ፲፬፤
ዲህ፡አድርገዋልና፡ከሹማምቱና፡ከለቆችም፡
ይኸን፡ትእዛዙን ፡ የተቀበሉ ፡ ሰዎች ፡ ከነገሩ
ዋቸው ፡ በኋላ ፡ እንዲህ ፡ አድርገዋልና ፡ በዚ
ያን ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእጅህ ፡ ይጥላቸ
ዋል ።
እኔ፡ ባርያህ ፡ ይኸን ፡ ሁሉ ፡ ባወቅሁ ፡ ጊዜ ፡ ፲፭፤፲፮፤
ከነርሳቸው ፡ ኰብልዬ ፡ መጣሁ ፡ እኔ ፡ ባርያህ ፡
እግዚአብሔርን ፡ የምፈራ ፡ ነኝና ፡ ሰማይን ፡
የፈጠረ ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ሌሊትና ፡ ቀን ፡
አገለግለዋለሁና ፡ በሰማው ፡ ጊዜ ፡ አገሩንና ፡
ሰውን ፡ ሁሉ ፡ የሚያስደነግጥ ፡ ይህንን ፡ ሥራ ፡
ከነርሳቸው ፡ ጋራ ፡ እሠራ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ላከኝ ።
አቤቱ ፡ አሁንም ፡ ከንተ ፡ ጋራ ፡ እኖራለሁ ፡ ፲፯፤
ነገር ፡ ግን ፡ እኔ ፡ ባርያህ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
እለምን ፡ ዘንድ ፡ ሌሊት ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡
እወጣለሁ ፡ መቼም ፡ መች ፡ የሠሩት ፡ ኀጢአ
ታቸውንም ፡ ይነግረኛል ።
መጥቼም ፡ ይኸንን ፡ እነግርሃለሁ ፡ ከሠራዊትህ ፡ ፲፰፤
ሁሉ ፡ ጋራ ፡ ትወጣለህ ፡ የሚከራከርህም ፡
የለም ።
ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ እስክትደርስ ፡ ድረስ ፡ በይ ፲፱፤
ሁዳ ፡ መካከል ፡ እወስድሃለሁ ፡ በመካከሏም ፡
ዙፋንን ፡ ትዘረጋለህ ፡ እረኛቸው ፡ እንደበተና
ቸው ፡ በጎች ፡ ፈጽመህ ፡ ገንዘብ ፡ ታደርጋቸዋ
ለህ ፡ ሥላሴ ፡ ለእኔ ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ ፈጽ
መው ፡ ነግረውኛልና ፡ ሰዎችህን ፡ በፊትህ ፡
ውሻ ፡ ስንኳ ፡ በምላሱ ፡ አይልሳቸውም ፡ ይህ
ንን ፡ አውቄ ፡ እነግርህ ፡ ዘንድ ፡ ተላክሁ ።
ነገሯም ፡ በፊቱ ፡ ሆሎፎርኒስን ፡ ደስ ፡ አሰኘው ፡ ፳፤
ሰዎችም ፡ ሁሉ ፡ ጥበቧን ፡ አደነቁ ።
ከምድር ፡ ዳርቻ ፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ ፳፩፤
በነገሩ ፡ ጥበብና ፡ በፊቷ ፡ ደም ፡ ግባት ፡ እንደ
ዚች ፡ ሴት ፡ ያለ ፡ የለም ፡ አሉ ።
ሆሎፎርኒስም ፡ በሥልጣናችን ፡ ጸንተሽ ፡ ትኖሪ ፡ ፳፪፤
ዘንድ ፡ ከወገኖችሽ ፡ አስቀድሞ ፡ የላከሽ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ በጎ ፡ ነገርን ፡ አደረገልሽ ፡ ጌታ
ዬን ፡ ለከዱ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ሞት ፡ መቃብር ፡
ይገባቸዋል ፡ አላት ።
አሁንም ፡ አንቺ ፡ መልክም ፡ ሰው ፡ ነሽ ፡ በቃ ፳፫፤
ልሽም ፡ የከበርሽ ፡ እንዳልሽው ፡ ከደረግሽ ፡
ፈጣሪሽ ፡ ፈጣሪዬ ፡ ይሆነኛል ፡ አንቺም ፡ በና
ቡከደነፆር ፡ ቤት ፡ ትቀመጫለሽ ፡ ስምሽም ፡
በገሩ ፡ ሁሉ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩፤ የብር ፡ ዕቃ ፡ ወደሚቀመጥበት ፡ ድንኳን ፡ ያገ
ቧት ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፡ ለርሱም ፡ ከሚያዘጋጁት ፡
ምግብ ይመግቧት ፡ ዘንድ ፡ እርሱ ፡ ከሚጠ
ጣው ፡ መጠጥም ፡ ያጠጧት ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ።
፪፤ ዮዲትም ፡ ከመጣሁት ፡ እህል ፡ እመገበለሁ ፡
እንጂ ፡ ኃጢአት ፡ እንዳይሆንብኝ ፡ ከርሱ ፡ አል
መገብም ፡ አለች ።
፫፤ ሆሎፎርኒስም ፡ ያመጣሽውስ ፡ ቢያልቅብሽ ፡ እን
ደርሱ ፡ ያለ ፡ ከየት ፡ አምጥተን ፡ እንሰጥሻለን ፡
ከወገኖችሽ ፡ ስንኳ ፡ ካንቺ ፡ ጋራ ፡ ሰው ፡ የለም ፡
አላት ።
፬፤ ዮዲትም ፡ እግዚአብሔር ፡ በኔ ፡ ቃል ፡ የመከረ
ውን ፡ እስኪያደርግ ፡ ድረስ ፡ እኔ ፡ ባሪያህ ፡ ያመ
ጣሁትን ፡ እንዳልጨርስ ፡ ጌታዬ ፡ በረከትህን ፡
አለችው ።
፭፤ የሆሎፎርኒስም ፡ አሽከሮች ፡ ወደ ፡ ድንኳኑ ፡
አገቧት ፡ እስከ ፡ ሌሊት ፡ እኩሌታም ፡ ድረስ ፡
ተኝታ ፡ አደረች ።
፮፤ ከእንቅልፏም ፡ ከተቀሰቀሰች ፡ በኋላ ፡ በሌሊት ፡
እኩሌታ ፡ ተነሥታ ፡ እኔ ፡ ባሪያህ ፡ እጸልይ ፡
ዘንድ ፡ እንዲያሰናብቱኝ ፡ እዘዝልኝ ፡ ብላ ፡ ወደ ፡
ሆሎፎርኒስ ፡ ላከች ።
፯፤ ሆሎፎርኒስም ፡ እንዳይከለክሏት ፡ የሚጠብቋ
ትን ፡ ሰዎች ፡ አዘዛቸው ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በሰ
ፈር ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ አደረች ፡ በሌሊት ፡ ወጥታ ፡
ወደ ፡ ቤሐሌዋ ፡ በረሃ ፡ ትወርድ ፡ ነበር ፡ ሌሊ
ትም ፡ በሠፈሩ ፡ ባለ ፡ ምንጭ ፡ ውኃ ፡ ትታጠብ ፡
ነበር ፡ ሌሊትም ፡ ወጥታ ፡ በምንጩ ፡ ውኃ ፡
ትጠመቅ ፡ ነበር ።
፰፤ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ፈጣሪ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
ትለምን ፡ ዘንድ ፡ በወጣች ፡ ጊዜ ፡ የወገኖቿ ፡
ልጆች ፡ በሚከብሩ ፡ ገንዘብ ፡ ጐዳናዋን ፡ ያቃ
ናላት ፡ ነበር ።
፱፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ትመለስ ፡ ነበር ፡ በከተማም ፡ ከኃ
ጢአት ፡ የነፃች ፡ ሁና ፡ ትቀመጥ ፡ ነበር ፡ ማታ ፡
ማታም ፡ ትመገብ ፡ ነበር ።
፲፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በራተኛይቱ ፡ ቀን ፡ ሆሎፎርኒስ ፡
ለአሽከሮቹ ፡ ለብቻቸው ፡ ምሳ ፡ አደረገ ፡ ሌላ ፡
ሰው ፡ ማንን ፡ ወደ ፡ ምሳ ፡ አልጠራም ።
፲፩፤ ገንዘቡ ፡ ሁሉ ፡ በርሱ ፡ ያለ ፡ ባለሚሉ ፡ የሆነ ፡
ሹሙ ፡ በግዋን ፡ በንተ ፡ ዘንድ ፡ ያለች ፡ ያችን ፡
ዕብራዊት ፡ ሴት ፡ ወደኛ ፡ ትመጣ ፡ ዘንድ ፡ አባ
ብልልኝ ፡ ከኛ ፡ ጋራ ፡ ትብላ ፡ ትጠጣ ፡ እንዲህ ፡
ያለች ፡ ሴት ፡ አግኝተን ፡ ባንናገራት ።
፲፪፤ ለኛ ፡ እፍረታችን ፡ ነውና ፡ አግኝተንም ፡ ብንተ
ዋት ፡ ይስቁብናልና ፡ ሄደህ ፡ ንገራት ፡ አለው ።
፲፫፤ ባግዋም ፡ ከሆሎፎርኒስ ፡ ዘንድ ፡ ወጥቶ ፡ ወደ
ርሷ ፡ ገብቶ ፡ መልክ ፡ መልካም ፡ የሆንሽ ፡ አንቺ ፡
ልጅ ፡ ወደ ፡ ጌታዬ ፡ መምጣትን ፡ እምቢ ፡ አት
በዪ ፡ በርሱ ፡ ዘንድ ፡ ትከብሪአለሽ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡
ወይንንም ፡ ጠጥተሽ ፡ ደስ ፡ ይልሻል ፡ በናቡከ
ደነፆር ፡ ቤት ፡ ከሚቆሙት ፡ ከናቡከደነፆር ፡
ሚስቶች ፡ እንደ ፡ አንዲቱ ፡ ትሆኛለሽ ፡ አላት ።
ዮዲትም ፡ እኔ ፡ ምን ፡ ቁም ፡ ነገር ፡ ነኝ ፡ መል ፲፬፤
ኬስ ፡ ምንድነው ፡ ጌታዬን ፡ እከራከረው ፡ ዘንድ ፡
ዘመዴስ ፡ ማነው ፡ የወደድከውን ፡ ሁሉ ፡ በፊ
ትህ ፡ ፈጥኜ ፡ አደርጋለሁ ፡ እስክሞት ፡ ድረስ ፡
ለኔም ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ይሆንልኛል ፡ አለችው ።
ተነሥታ ፡ አጌጠች ፡ ልብሷንም ፡ ለበሰች ፡ የሴ ፲፭፤
ቶችንም ፡ ጌጥ ፡ ሁሉ ፡ አጌጠች ፡ ብላቴናዋም ፡
ከርሷ ፡ ጋራ ፡ ሄደች ፡ ከባግዋ ፡ የተቀበለችውን ፡
በማደሪያዋ ፡ ያነጠፈላትን ፡ ምሳም ፡ ባደረገች ፡
ጊዜ ፡ በላዩ ፡ የምትቀመጥበት ፡ ምንጣፏን ፡ በሆ
ሎፎርኒስ ፡ ፊት ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ አነጠፈችላት ።
ከወንድ ፡ የተለየች ፡ ዮዲትም ፡ ወደርሱ ፡ ገባች ፡ ፲፮፤
የሆሎፎርኒስም ፡ ልቡናው ፡ በርሷ ፡ ታወከ ፡
ከርሷ ፡ ጋራ ፡ ይተኛ ፡ ዘንድ ፡ ሰውነቱም ፡ ፈጽማ ፡
ወደደች ፡ ካየት ፡ ጀምሮ ፡ እርሷን ፡ እስከሚያ
ባብልበት ፡ ጊዜ ፡ ድረስ ፡ ይጠብቃት ፡ ነበር ።
ሆሎፎርኒስም ፡ ዮዲትን ፡ ከኛ ፡ ጋራ ፡ ጠጥተሽ ፡ ፲፯፤
ደስ ፡ ይበልሽ ፡ አላት ።
ዮዲትም ፡ ከተወለድሁ ፡ ጀምሮ ፡ ከዘመኔ ፡ ሁሉ ፡ ፲፰፤
ይልቅ ፡ በኔ ፡ ያለች ፡ ሰውነት ፡ ዛሬ ፡ ከብራለ
ችና ፡ ጌታዬ ፡ እጠጣለሁ ፡ አለችው ።
ተነሥታ ፡ ጠጣች ፡ ባሪያዋም ፡ ያዘጋጀችላትን ፡ ፲፱፤
በፊቱ ፡ በላች ።
ሆሎፎርኒስም ፡ ስለርሷ ፡ ደስ ፡ አለው ፡ ከተፈ ፳፤
ጠረ ፡ ከተወለደም ፡ ጀምሮ ፡ አንዲት ፡ ቀን ፡
ስንኳ ፡ እንደሱ ፡ ያለ ፡ ያልጠጣውን ፡ መጠጥ ፡
አብዝቶ ፡ ብዙ ፡ ወይን ፡ ጠጣ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

በመሸም ፡ ጊዜ ፡ አሽከሮቹ ፡ ፈጥነው ፡ ሰውን ፡ ፩፤
አስወጡ ፡ ባግዋም ፡ ከወደ ፡ ውጭ ፡ በላያቸው ፡
ድንኳኑን ፡ ቈለፈ ፡ በጌታውም ፡ ፊት ፡ የቆሙ ፡
አሽከሮቹን ፡ አስወጥቶ ፡ ሰደዳቸው ፡ ፈጽመው ፡
ስለ ፡ ጠጡ ፡ ሁሉም ፡ ደክመዋልና ፡ ወደ ፡ ማደ
ሪያቸው ፡ ገቡ ።
ዮዲት ፡ ብቻዋን ፡ ቀረች ፡ ወይንን ፡ አብዝቶ ፡ ፪፤
ጠጥቶ ፡ ሰክሮ ፡ ነበርና ፡ ሆሎፎርኒስም ፡ በድን
ኳኑ ፡ ውስጥ ፡ ተኝቶ ፡ ነበር ።
ዮዲትም ፡ ባሪያዋን ፡ ወደ ፡ ውጪ ፡ ወጥታ ፡ ፫፤
በማደሪያዋ ፡ ትቆም ፡ ዘንድ ፡ አዘዘቻት ፡ ወደ
ምትጸልይበት ፡ እወጣለሁ ፡ ብላታለችና ፡ እንደ ፡
ወትሮዋም ፡ ትጠብቃት ፡ ዘንድ ፡ አዘዘቻት ፡
ለባግዋም ፡ እንደዚሁ ፡ ነገረችው ።
ሁሉም ፡ ከርሷ ፡ ዘንድ ፡ ወጡ ፡ ታናሽም ፡ ታላ ፬፤
ቅም ፡ ቢሆን ፡ በልፍኙ ፡ የቀረ ፡ የለም ፡ ዮዲ
ትም ፡ ተነሥታ ፡ በመኝታው ፡ አጠገብ ፡ ቆመች ።
በልቧም ፡ የፍጹም ፡ ኃይል ፡ ፈጣሪ ፡ አቤቱ ፡
ይኸንን ፡ ነገር ፡ እዩ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡
ትል ፡ ዘንድ ፡ በዚች ፡ ጊዜ ፡ በኔ ፡ እጅ ፡ ኃይል
ህን ፡ አድርግ ።
ማደሪያህ ፡ እስራኤልን ፡ በምታነሣ ፡ ገንዘብ ፡ ፭፤
ጊዜው ፡ ደርሷልና ፡ በኛ ፡ የተነሡ ፡ ጠላቶች ፡
በሚጠፉ ፡ ገንዘብ ፡ አሳቤንም ፡ ፈጽምልኝ ፡

አለች ።
፮፤ ወደ ፡ ሆሎፎርኒስ ፡ መኝታ ፡ ወደ ፡ ትራሱ ፡
ሄደች ፡ ሰይፉንም ፡ መዛ ፡ በራስጌው ፡ ቆመች ።
፯፤ የራሱን ፡ ጠጉር ፡ ይዛ ፡ የእስራኤል ፡ ፈጣሪ ፡
አቤቱ ፡ ዛሬ ፡ አጽናኝ ፡ አለች ።
፰፤ በኃይሏ ፡ ሁለት ፡ ጊዜ ፡ አንገቱን ፡ መታችው ፡
ራሱንም ፡ ከርሱ ፡ ቈረጠችው ።
፱፤ ሬሳውንም ፡ ከመኝታው ፡ ላይ ፡ አንሥታ ፡ ወደ ፡
ምድር ፡ ጣለችው ፡ ጥቂትም ፡ አረፈች ፡ ወጥታ ፡
ለብላቴናዋ ፡ የሆሎፎርኒስን ፡ ቸብቸብ ፡ ሰጠቻት ።
፲፤ እህል ፡ በምትይዝበት ፡ ራዎት ፡ ጨመረችው ፡
ለጸሎት ፡ እንዳስለመዱ ፡ ሁለቱ ፡ ሁሉ ፡ አንድ
ነት ፡ ወጡ ፡ ከከተማውም ፡ አልፈው ፡ ወደ ፡
በረሃ ፡ ሔዱ ፡ ወደ ፡ ቤጤሉዋ ፡ አቀበት ፡ ወጡ ፡
ወዳገሩ ፡ በርም ፡ ደረሱ ።
፲፩፤ ዛሬ ፡ ኃይልን ፡ እንዳደረገ ፡ ዳግመኛ ፡ ለእስራ
ኤል ፡ ጠላቶቻቸው ፡ ላይ ፡ ጽናትና ፡ ኃይልን ፡
ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከኛ ፡ ጋራ ፡
በረድኤት ፡ አለና ፡ ዮዲትም ፡ በሩቅ ፡ ሆና ፡
በር ፡ የሚጠብቁ ፡ ዘበኞችን ፡ በሩን ፡ ክፈቱልኝ ፡
አለቻቸው ።
፲፪፤ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ባገር ፡ ያሉ ፡ ሰዎች ፡ ቃሏን ፡
በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ አገሩ ፡ በር ፡ ፈጥነው ፡
ወረዱ ፡ ያገር ፡ አለቆችንም ፡ ጠሩ ፡ እንደተመ
ለሰች ፡ አድንቀዋልና ።
፲፫፤ ታናሹም ፡ ታላቁም ፡ ሁሉ ፡ ሮጠው ፡ ሔዱ ፡
በሩን ፡ ከፍተው ፡ ተቀበሏት ፡ እሳት ፡ አንድ
ደው ፡ ፋና ፡ አብርተው ፡ ከበቧት ።
፲፬፤ ጠላቶቹን ፡ በዚች ፡ ሌሊት ፡ በእጄ ፡ አጠፋቸው ፡
እንጂ ፡ ምሕረቱንና ፡ ይቅርታውን ፡ ከእስራ
ኤል ፡ አላራቀምና ፡ በታላቅ ፡ ቃል ፡ እግዚአብ
ሔርን ፡ አመስግኑት ፡ አለቻቸው ።
፲፭፤ ራሱን ፡ ከርከ፡ ፡ አውጥታ ፡ አሳየቻቸው ፡ የና
ቡከደነፆር ፡ የሠራዊቱ ፡ አለቃ ፡ የቢትወደዱ ፡
ራስ ፡ እነሆ ፡ ይኸው ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ ተንተር
ሶት ፡ የሚተኛበት ፡ ሰይፉም ፡ እነሆ ፡ ይኸው ፡
እግዚአብሔር ፡ በኔ ፡ አድሮ ፡ ገደለው ፡ አለ
ቻቸው ።
፲፮፤ እንዲሞት ፡ በመልኬ ፡ አስተው ፡ ዘንድ ፡ በሔ
ድሁበት ፡ ጐዳና ፡ የጠበቀኝ ፡ በኔም ፡ ኃጢአ
ትና ፡ በደልን ፡ ጕስቍልናን ፡ ያላደረገ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ሕያው ፡ ነው ፡ አለቻቸው ።
፲፯፤ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ፈጽመው ፡ ደነገጡ ፡ ለእግዚ
አብሔርም ፡ ፈጽመው ፡ ሰገዱ ፡ አንድነት ፡ እን
ዲህ ፡ አሉ ፡ ዛሬ ፡ በዚህች ፡ ቀን ፡ የወገኖቸ
ህን ፡ ጠላቶች ፡ ያጠፋሃቸው ፡ አንተ ፡ ፈጣሪያ
ችን ፡ የተመሰገንህ ፡ ነህ ፡ አሉ ።
፲፰፤ ዖዝያንም ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ከሚኖሩ ፡ ሴቶች ፡
ይልቅ ፡ አንቺ ፡ ልጄ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ደግ ፡
ፍጥረቱ ፡ ነሽ ።
፲፱፤ ለዘላለሙ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ኃይል ፡ እያሰቡ ፡
ምስጋናሽ ፡ ከሰው ፡ ልቡና ፡ አይጠፋምና ፡ ምድ
ርና ፡ ሰማይን ፡ የፈጠረ ፡ የጠላቶቻችንን ፡ አለቃ ፡
ቸብቸብ ፡ ትቆርጪ ፡ ዘንድ ፡ የረዳሽ ፡ እግዚአ
ብሔርም ፡ የተመሰገነ ፡ ነው ።
እግዚአብሔርም ፡ ከምሽን ፡ ለዘለዓለሙ ፡ እን ፳፤
ዲጠራ ፡ ያድርግልሽ ፡ ስለወገኖችሽ ፡ መከራ ፡
አንቺ ፡ ልሙት ፡ ብለሽ ፡ ወጣሽ ፡ እንጂ ፡ በፈ
ጣሪያችን ፡ በእግዚአብሔርም ፡ ራት ፡ አቅን
ተሽ ፡ ሔድሽ ፡ እንጂ ፡ ለሰውነትሽ ፡ አልራራ
ሽምና ፡ በቸርነቱ ፡ ይመልከትሽ ፡ አላት ፡ ሕዝ
ቡም ፡ ሁሉ ፡ እውነት ፡ ነው ፡ እውነት ፡ ነው ፡
አሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

ዮዲትም ፡ ወንድሞቻችን ፡ ስሙኝ ፡ ይኸንን ፡ ፩፤
ቸብቸብ ፡ ይዛችሁ ፡ በምባው ፡ መከታ ፡ ላይ ፡
ስቀሉት ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ሲነጋ ፡ ፀሐይ ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ። ፪፤
ሁላችሁም ፡ መሣሪያችሁን ፡ ያዙ ፡ አርበኞች ፡ ፫፤
የሆኑ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ከምባ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡
ይውጡ ፡ አለቃም ፡ ሹሙ ፡ የኃያላኑ ፡ አሽከ
ሮች ፡ ዘበኞች ፡ ወዳሉበት ፡ ምድርም ፡ በወረ
ዳችሁ ፡ ጊዜ ፡ ሳትወርዱ ፡ ሁላችሁም ፡ መሣሪ
ያችሁን ፡ ፈጽማችሁ ፡ ያዙ ፡ ከይዋችሁ ፡ በኋላ ፡
ዘበኞች ፡ የናቡከደነፆርን ፡ የሠራዊቱን ፡ አለ
ቆች ፡ ሠራዊቱንም ፡ ያስነሡ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡
ሠፈራቸው ፡ ይሄዳሉ ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡
ሆሎፎርኒስ ፡ ድንኳን ፡ ይሮጣሉ ፡ አያገኙትም ፡
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ፈርተው ፡ ከፊታችሁ ፡ ይሸሻሉ ።
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ እናንተ ፡ ተከተሏቸው ፡ በእስ ፬፤
ራኤል ፡ አውራጃ ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ይከ
ተሏቸው ፡ በጐደናቸው ፡ ሁሉ ፡ ቃርሚቸው ።
ይኸንን ፡ ሳታደርጉ ፡ የእስራኤልን ፡ ወገን ፡ እን ፭፤
ደከደው ፡ ከኛም ፡ ጋራ ፡ ይሞት ፡ ዘንድ ፡ እር
ሱን ፡ አሥሮ ፡ወደኛ ፡ እንደላከው ፡ እርሱ ፡
እንደ ፡ ሆነ ፡ አይቶ ፡ ያውቅ ፡ ዘንድ ፡ የአሞኑን ፡
ሰው ፡ አኪዮርን ፡ ጥሩልኝ ፡ አለቻቸው ።
አኪዮርንም ፡ ከዖዝያን ፡ቤት ፡ ጠሩት ፡ መጥቶ ፡ ፮፤
የሆሎፎርኒስን ፡ ራስ ፡ በዮዲት ፡ እጅ ፡ ባየ ፡
ጊዜ ፡ ሰውነቱ ፡ ደንግጦ ፡ በሕዝቡ ፡ መካከል ፡
በግምባሩ ፡ ፍግግም ፡ ብሎ ፡ ወደቀ ።
በነሡትም ፡ ጊዜ ፡ በዮዲት ፡ እግር ፡ ላይ ፡ ፯፤
ወደቀ ፡ እግር ፡ ከግምባር ፡ አድርጎ ፡ሰገደ ፡ ከሕ
ዝቡ ፡ ሁሉና ፡ ከይሁዳ ፡ መኳንንት ፡ ሁሉ ፡
ይልቅ ፡ አንቺ ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ደግ ፡ ፍጥረት ፡
ነሽ ፡ ስምሽንም ፡ ሰምተው ፡ ይደነግጣሉ ፡
አላት ።
አሁንም ፡ በነዚህ ፡ ወራት ፡ ያደረግሺውን ፡ ንገ ፰፤
ሪኝ ፡ አላት ። ዮዲትም ፡ ከወጣች ፡ ጀምሮ ፡ እስ
ክትመለስ ፡ ድረስ ፡ ያደረገችውን ፡ ሁሉ ፡ በሕ
ዝቡ ፡ መካከል ፡ ነገረችው ።
ነገሯን ፡ ተናግራ ፡ በጨረሰች ፡ ጊዜ ፡ ሕዝቡ ፡ ፱፤
ሁሉ ፡ ቃላቸውን ፡ አሰምተው ፡ ደነፉ ፡ በያምባ
ቸው ፡ ሆነው ፡ የተድላ ፡ የደስታ ፡ ቃል ፡ ተናገሩ ።
አኪዮርም ፡ እግዚአብሔር ፡ ለእስራኤል ፡ ያደ ፲፤
ረገውን ፡ ተአምራት ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ፈጽሞ ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ አምኖ ፡ ተገዘረ ። እስከ ፡ ዛሬ ፡

ድረስ ፡ በሃይማኖት ፡ አንድ ፡ ሆነ ።
፲፩፤ በነጋም ፡ ጊዜ ፡ የሆሎፎርኒስን ፡ ራስ ፡ በተራ
ዳው ፡ ላይ ፡ ሰቀለው ፡ ወንዶቹም ፡ ሁሉ ፡ መሣ
ሪያቸውን ፡ ይዘው ፡ ወጥተው ፡ በተራራው ፡
ዓቀበት ፡ አንፃር ፡ ከበቧቸው ።
፲፪፤ የናቡከደነፆርም ፡ አሽከሮች ፡ ባዩዋቸው ፡ ጊዜ ፡
ወደ ፡ ሹሞቻቸው ፡ ላኩ ።
፲፫፤ ሹማምቶቻቸውና ፡ አለቆቻቸውም ፡ ወደ ፡ ሆሎ
ፎርኒስ ፡ ድንኳን ፡ መጡ ፡ እለዚህ ፡ ባሮች ፡ ተደ
ፋፍረው ፡ ወርደዋልና ፡ እኛንም ፡ ይወጉን ፡
ዘንድ ፡ ወንድ ፡ ወንድ ፡ መስለዋልና ፡ ሹሙን ፡
ጌታችንን ፡ ከንቅልፉ ፡ ቀስቅሰው ፡ አሉት ።
፲፬፤ ከዮዲት ፡ ጋራ ፡ የተኛ ፡ መስሎታልና ፡ በግ
ዋም ፡ ጉብቶ ፡ በድንኳኑ ፡ አንፃር ፡ ያለ ፡ በሩን ፡
ከፈተ ።
፲፭፤ ቃል ፡ የሚመልስለት ፡ ሰው ፡ ባጣ ፡ ጊዜ ፡ ድን
ኳኑን ፡ ተርትሮ ፡ ገባ ፡ ራሱ ፡ ተቈርጦ ፡ ሬሳውን ፡
በምድር ፡ ላይ ፡ ወድቆ ፡ አገኘው ።
፲፮፤ ልብሱን ፡ ቀዶ ፡ እያለቀሰ ፡ ቃሉን ፡ አሰምቶ ፡
ፈጽሞ ፡ ጮኸ ።
፲፯፤ ዮዲት ፡ ወደምታድርበትም ፡ ድንኳን ፡ ገባ ፡
ነገር ፡ ግን ፡ አላገኛትም ፡ ወደ ፡ ሕዝቡም ፡ ሄዶ ፡
ጮኸላቸው ።
፲፰፤ እነዚህ ፡ ባሮች ፡ ከዱን ፡ እነሆ ፡ የሆሎፎርኒስ ፡
ሬሳው ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ወድቋልና ፡ ራሱም ፡
በላዩ ፡ የለምና ፡ አንዲት ፡ ዕብራዊት ፡ ሴት ፡ በን
ጉሡ ፡ በናቡከደነፆር ፡ ወገን ፡ ላይ ፡ ኀፍረትን ፡
አድርጋለች ፡ አላቸው ።
፲፱፤ የናቡከደነፆር ፡ የሠራዊቱ ፡ አለቆች ፡ ይህንን ፡
ነገር ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ልብሳቸውን ፡ ቀደዱ ፡ ሰው
ነታቸውም ፡ ፈጽማ ፡ ደነገጠች ፡ ቃላቸውን ፡
አሰምተው ፡ በሰፈር ፡ መካከል ፡ ፈጽመው ፡
ጮሁ ።

ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩፤ በሰፈርም ፡ ያሉ ፡ ሰዎች ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ እነ
ርሳቸውም ፡ ስለ ፡ ተደረገው ፡ ነገር ፡ ደነገጡ ።
፪፤ ፍርሃት ፡ እንቅጥቅጥ ፡ ያዛቸው ፡ ሁሉም ፡ ደን
ግጠው ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳና ፡ ወደ ፡ ጐዳና ፡
ወደ ፡ ተራራም ፡ አንድነት ፡ ሸሹ ፡ እንጂ ፡ ከዚህ ፡
በኋላ ፡ ከባልንጀራው ፡ ጋራ ፡ የቆመ ፡ ሰው ፡
የለም ።
፫፤ በቤጤሌዋ ፡ ዙሪያ ፡ በተራራውና ፡ በሰፈር ፡
ያሉ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ እነርሳቸውም ፡ ተሸብረው ፡
ሸሹ ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ አርበኞች ፡ ሰዎች ፡ የሚ
ሆኑ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ተነሥተው ፡
ተከተሏቸው ።
፬፤ ዖዝያንም ፡ የሆነውን ፡ ሁሉ ፡ ይናገሩ ፡ ዘንድ ፡
ሁሉም ፡ ይረዱ ፡ ዘንድ ፡ ጠላቶቻቸውንም ፡
ተከትለው ፡ ያጠፏቸው ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ቤቢና ፡
ወደ ፡ ሴሎ ፡ መስቴምስ ፡ ወደ ፡ ቆላና ፡ ወደ ፡
ኮቢ ፡ ወደ ፡ እስራኤልም ፡ አውራጃ ፡ ሁሉ ፡ ላከ።
፭፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ሁሉም ፡
አንድነት ፡ እስከ ፡ ኮቤ ፡ ድረስ ፡ ተከትለው ፡
አጠፏቸው ፡ በጠላቶቻቸው ፡ ሰፈር ፡ የሆነውን ፡
ነገር ፡ ነግረዋቸዋልና ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ከያውራ
ጃው ፡ የመጡ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ እንደዚሁ ፡ አጠፏ
ቸው ፡ ከገለዓድና ፡ ከገሊላም ፡ የመጡ ፡ ሰዎች ፡
ተከተሏቸው ፡ ከውራጃዋና ፡ ከደማስቆ ፡ እስ
ኪሻገሩ ፡ ድረስ ፡ ደርሰው ፡ ጽኑ ፡ ሰልፍ ፡ አድ
ርገው ፡ አጠፏቸው ።
በቤጤሌዋም ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ፮፤
አርበኛው ፡ ሰፈር ፡ ወርደው ፡ ገንዘባቸውን ፡
በዘበዝዋቸው ፡ ፈጽመውም ፡ ከበሩ ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ከተዋጉ ፡ ፯፤
በት ፡ ተመለሱ ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ ሰፌ ፡ አውራጃ
ቸውን ፡ ይዘውባቸው ፡ ነበርና ፡ በቆላና ፡ በደጋ ፡
ያለ ፡ እምባቸውንና ፡ የቀረ ፡ በታቸውን ፡ ሁሉ ፡
ገንዘብ ፡ አደረጉ ።
ከፍ ፡ ያለ ፡ የካህን ፡ አለቃ ፡ ኢዮአቄም ፡ መጣ ፡ ፰፤
በኢየሩሳሌም ፡ የሚኖሩ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡
ሽማግሎችም ፡ እግዚአብሔር ፡ ለእስራኤል ፡
ያደረገውን ፡ በጎ ፡ ረድኤት ፡ ያዩ ፡ ዘንድ ፡ ዮዲ
ትንም ፡ ያይዋት ፡ ዘንድ ፡ ከሷም ፡ ጋራ ፡ ተድላ ፡
ደስታ ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ወዳምባው ፡ መጡ ።
ወደርሷ ፡ በገቡ ፡ ጊዜ ፡ ሁሉም ፡ አንድነት ፡ ፱፤
መረቋት ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ላይ ፡ አንቺ ፡ እመ
ቤት ፡ ነሽ ፡ የእስራኤልም ፡ ክብራቸው ፡ ገናንነ
ታቸው ፡ አንቺ ፡ ነሽ ፡ የወገኖቻችንም ፡ መመ
ኪያ ፡ አንቺ ፡ ነሽ ።
ይህ ፡ ሁሉ ፡ በእጅሽ ፡ ተደርጓልና ፡ ይህንንም ፡ ፲፤
በጎ ፡ ነገር ፡ ለእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ አድርገሻልና ፡
እግዚአብሔርም ፡ እነሳቸውን ፡ ወዷልና ፡ ሁሉን ፡
በሚገዛ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ለዘለዓለሙ ፡
የከበርሽ ፡ ሁኚ ፡ አሏት ።
ሕዝቡም ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ ሰፈራቸውን ፡ በረበሩ ፡ ፲፩፤
ለዮዲትም ፡ የሆሎፎርኒስን ፡ ድንኳን ፡ የብ
ሩን ፡ ዕቃ ፡ ሁሉ ፡ ዙፋኑን ፡ ያለውንም ፡ ገንዘብ ፡
ሁሉ ፡ ሰጧት ፡ ወሰደች ፡ በበቅሎዋ ፡ ተቀመ
ጠች ፡ ሠረገላዎቹንም ፡ ነድታ ፡ ከርሷ ፡ ጋራ ፡
ወደ ፡ አገሯ ፡ አገባች ።
የእስራኤልም ፡ ሴቶች ፡ ሁሉ ፡ ያይዋት ፡ ዘንድ ፡ ፲፪፤
ይመርቋት ፡ ዘንድ ፡ ሮጠው ፡ ወጡ ፡ ደግ ፡ በዓ
ልንም ፡ አደረጉላት ፡ ዘምባባውን ፡ በጅዋ ፡
ያዘች ፡ ከርሷ ፡ ጋራ ፡ ላሉ ፡ ሴቶችም ፡ ሰጠች ፡
እነርሱም ፡ አመሰገንዋት ።
በሕዝቡ ፡ ፊት ፡ ሔደች ፡ የሴቶችም ፡ ሁሉ ፡ ፲፫፤
አለቃቸው ፡ እርሷ ፡ ናት ፡ የእስራኤልም ፡ አርበ
ኞች ፡ ሁሉ ፡ ፈጽመው ፡ እያመሰገንዋት ፡ መሣ
ሪያቸውን ፡ ይዘው ፡ ተከተልዋት ።

ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

ዮዲትም ፡ ይቺን ፡ ምስጋና ፡ በሁላቸው ፡ ፩፤
በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ዘንድ ፡ ተናገረች ፡ ሕዝ
ቡም ፡ ሁሉ ፡ ይቺን ፡ ምስጋና ፡ ተናገሩ ።
ዮዲትም ፡ ፈጣሪያችን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ከበሮ ፡ ፪፤
እየመታችሁ ፡ አመስግኑት ፡ ጸናጽልም ፡ እየመ
ታችሁ ፡ አመስግኑት ፡ በገና ፡ እየደረደራችሁ ፡

ምስጋና፡ኢያመስግናችሁ፡አክብሩት፡አግኑት።
፫፤ እግዚአብሔር፡ ጠላትን፡ ያጠፋልና ።
፬፤ ስሙም፡ አሸናፊ፡ ይባላልና፡ ስሙንም፡ አመስ
ግኑ ፡ እሱ ፡ ከሠራዊቱ ፡ ከመላእክት ፡ ጋራ ፡
በሕዝቡ ፡ መካከል ፡ ሆኖ ፡ ከተከተሉን ፡ ከአሕ
ዛብ ፡ አድኖናልና ፡ ስሙን ፡ አመስግኑት ።
፭፤ አርበኞቹ ፡ ከመስዕ ፡ አጠገብ ፡ ከተራራው ፡
መጡ ፡ ከብዙ ፡ ሠራዊቶችም ፡ ጋራ ፡ ወጡ ፡ በብ
ዛታቸውም ፡ ፈሳሹን ፡ አቆሙት ፡ ፈረሶቻቸ
ውም ፡ ኮረብታውን ፡ ሸፈኑት ።
፮፤ አውራጃችንን ፡ በእሳት ፡ ያቃጥሉ ፡ ዘንድ ፡ አቃ
ጥሉ ፡ በጦርም ፡ ጕልማሶቻችንን ፡ ይገድሉ ፡
ዘንድ ፡ ግደሉ ፡ ልጆቻችንንም ፡ ቆነጃጅቱንም ፡
ይማርኩ ፡ ዘንድ ፡ ማርኩ ፡ ብለው ፡ ነበር ።
፯፤ ነገር ፡ ግን ፡ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ እግዚአብሔር ፡
በዮዲት ፡ እጅ ፡ አጠፋቸው ።
፰፤ አርበኛቸው ፡ በጕልማሳ ፡ እጅ ፡ ድል ፡ አልተነ
ሣምና ፡ የጢቤናም ፡ ልጆች ፡ ያጠኑቸው ፡ አይ
ደሉምና ፡ የሚራሪ ፡ ልጅ ፡ ዮዲት ፡ በደም ፡
ግባቷ ፡ አጠፋችው ፡ እንጂ ፡ ከፍ ፡ ያሉ ፡ አርበ
ኞችም ፡ ድል ፡ የነሷቸው ፡ አይደሉምና ፡ ነገር ፡
ግን ፡ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ እግዚአብሔር ፡ በዮዲት ፡
እጅ ፡ አጠፋቸው ።
፱፤ የድኅነቷን ፡ ልብስ ፡ በሚያገዙ ፡ በእስራኤል ፡
ዘንድ ፡ ትታ ፡ ሄደች ።
፲፤ ፊቷንም ፡ ሽቱ ፡ ተቀባች ፡ ራስዋን ፡ ተሠርታ ፡
ሰርመዴ ፡ አደረገች ፡ ሆሎፎርኒስን ፡ ለማሳት ፡
የሐር ፡ ልብስንም ፡ ለበሰች ።
፲፩፤ ጫማዋንም ፡ ተጫማች ፡ በደም ፡ ግባቷም ፡ ዓይ
ኑን ፡ በዘበዘችው ፡ ደም ፡ ግባቷም ፡ ሰውነቱን ፡
ማረከች ፡ ሰይፍም ፡ በአንገቱ ፡ ሄደ ።
፲፪፤ ከመደፋፈርዋ፡የተነሣ፡የፋርስ፡ሰዎች፡ደነገጡ፡
ከመጨከንዋም፡የተነሣ፡የሚዶን፡ሰዎች፡ፈሩ።
፲፫፤ ያን ፡ ጊዜ ፡ ያዘኑ ፡ ወገኖቼ ፡ ደነፉ ፡ የተናቁ ፡
ወገኖቼም ፡ ፈርተው ፡ ነበር ፡ ደንግጠው ፡ ነበር ።
፲፬፤ የወገኖቼም ፡ ልጆች ፡ ቃላቸውን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡
አድርገው ፡ ተከትለው ፡ ወጓቸው ፡ አርበኞቻ
ችንም ፡ ወጓቸው ፡ ከእግዚአብሔር ፡ አርበኞች ፡
ከእስራኤልም ፡ የተነሣ ፡ ጠፉ ።
፲፭፤ ለእግዚአብሔር ፡ ምስጋና ፡ አቀርባለሁ ፡ ፈጽ
ሜም ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰግናለሁ ።
፲፮፤ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ገናና ፡ ነው ፡ ፈጽሞ ፡ የከ
በረ ፡ ነው ፡ ኃይሉም ፡ የተደነቀ ፡ ነው ።
፲፯፤ ይፈጠሩ ፡ ብለሀልና ፡ እነርሳቸውም ፡ ተፈጥረ
ዋልና ፡ ፍጥረትህ ፡ ሁሉ ፡ ይገዙልሃል ፡ መንፈስ
ረድኤትህን ፡ ሰድደህ ፡ እስራኤልም ፡ በረድ
ኤት ፡ ታደሱ ።
፲፰፤ ተራሮች ፡ ከመሠረታቸው ፡ ይነዋወጣሉና ፡
ውኆችም ፡ ይነዋወጣሉና ፡ አለቱም ፡ ገጸ ፡ መዓ
ትህ ፡ ከመገለጡ ፡ የተነሣ ፡ እንደ ፡ አደሮ ፡ ማር ፡
ይቀልጣልና ፡ ለቃልህም ፡ የማይታዘዝ ፡ የለም ።
በጎ ፡ መዓዛ ፡ አድርገህ ፡ ልትቀበለው ፡ መሥዋ ፲፱፤
ዕቱ ፡ ሁሉ ፡ አይበቃምና ፡ ስቡም ፡ ሁሉ ፡ ከቍ
ርባንህ ፡ ያንሣልና ፡ ዳግመኛም ፡ የሚፈሩህን ፡
ሰዎች ፡ ይቅር ፡ በላቸው ። እግዚአብሔርን ፡
የሚፈራው ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ሁልጊዜ ፡ ገናና ፡ ነው ።
በወገኖቼ ፡ በጠላትነት ፡ ለሚነሡ ፡ አሕዛብ ፡ ወዮ ፳፤
ላቸው ፡ የሚገዛ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ቍርጥ ፡
ፍርድ ፡ በሚደረግበት ፡ ቀን ፡ ተበቅሎ ፡ ያጠ
ፋቸዋል ።
በሰውነታቸውም ፡ ትልና ፡ እሳትን ፡ ያመጣብ ፳፩፤
ቸዋል ፡ በመከራም ፡ ተይዘው ፡ ለዘላለሙ ፡ ያለ
ቅሳሉ ።
እስራኤልም ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ በደረሱ ፡ ፳፪፤
ጊዜ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ሰገዱ ፡ ሕዝቡም ፡ ከኃ
ጢአት ፡ ራሳቸውን ፡ብንጹ ፡ ጊዜ ፡ በፈቃዳቸው ፡
የሚሰጡትን ፡ ገንዘባቸውንና ፡ ቍርባናቸውን ፡
አገቡ ።
ዮዲትም ፡ ሕዝቡ ፡ የሰጡት ፡ የሆሎፎርኒስን ፡ ፳፫፤
ገንዘብ ፡ አኖረች ።
ሕዝቡም ፡ በቤተ ፡ መቅደስ ፡ አንፃር ፡ ባለች ፡ ፳፬፤
በኢየሩሳሌም ፡ ባለ ፡ በቤተ ፡ መቅደስ ፡ ሦስት ፡
ወር ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ አደረጉ ፡ ዮዲትም ፡ ከነ
ርሳቸው ፡ ጋራ ፡ ተቀመጠች ።
ከዚያ ፡ ወራት ፡ በኋላ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ወደርስቱ ፡ ፳፭፤
ገባ ፡ ዮዲትም ፡ ወደ ፡ ቤጤሌዋ ፡ ተመልሳ ፡
በሥራዋ ፡ ጸንታ ፡ኖረች ፡ በዘመኗም ፡ በገሩ ፡
ሁሉ ፡ የከበረች ፡ ሆነች ።
የሚፈልጓትም ፡ ሰዎች ፡ ብዙ ፡ ነበሩ ፡ ባሏ ፡ ፳፮፤
ምናሴ ፡ ሞቶ ፡ በወገኖቹ ፡ ዘንድ ፡ ከተቀበረ ፡
ጀምሮ ፡ በሕይወት ፡ በኖረችበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡
በግብር ፡ ያወቃት ፡ ሰው ፡ የለም ።
ፈጽማ ፡ ገነነች ። ፳፯፤
በባሏ ፡ በምናሴ ፡ ቤት ፡ እስከ ፡ ታረጅ ፡ ድረስ ፡ ፳፰፤
ኖረች ፡ ዘመኖቿም ፡ መቶ ፡ አምስት ፡ ናቸው ፡
ያቺንም ፡ ብላቴናዋን ፡ ነፃ ፡ አወጣቻት ፡ በቤጤ
ሌዋ ፡ ሞታ ፡ በባሏ ፡ በምናሴ ፡ መቃብር ፡ ተቀ
በረች ።
የእስራኤልም ፡ ወገኖች ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ አለቀሱ ፳፱፤
ላት ፡ ገንዘቧንም ፡ ሳትሞት ፡ ለባሏ ፡ ለምናሴ ፡
አቅራቢያ ፡ ለሆኑ ፡ ለርሷ ፡ አቅራቢያ ፡ ለሆኑ ፡
ለዘመዶቿም ፡ ከፍላ ፡ ሰጠች ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ በዮዲት ፡ ፴፤
ዘመን ፡ ያስፈራቸው ፡ የለም ፡ ዳግመኛ ፡ ከሞ
ተች ፡ በኋላ ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ ያስፈራቸው ፡ የለም ።
ለእግዚአብሔር ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ክብር ፡ ምስ
ጋና ፡ ይግባውና ፡ ዮዲት ፡ የተናገረችው ፡ ነገር ፡
መላ ፡ ተፈጸመ ።

# መጽሐፈ ፡ አስቴር ።

፩፤ ከፍ ፡ ያለ ፡ ንጉሥ ፡ አርጤክስስ ፡ በነገሠ ፡ በሁ
ለተኛው ፡ ዓመት ፡ በኒሳን ፡ መበቻ ፡ የኢያዕር ፡
የሰሜኢ ፡ የቂስ ፡ ልጅ ፡ ከብንያም ፡ የተወለደ ፡
የአይሁድ ፡ ወገን ፡ ሰው ፡ የሚሆን ፡ መርዶክ
፪፤ ዮስ ፡ ሕልም ፡ አየ ፤ በሱሳ ፡ አገር ፡ ይኖር ፡
ነበር ፥ ሰውነቱም ፡ የገነነ ፡ ነበረ ፤ በንጉሡ ፡
፫፤ ቤት ፡ አደባባይ ፡ ይኖር ፡ ነበር ። ከተማረኩ ፡
ሰዎች ፡ ወገን ፡ ነበረ ፤ ከይሁዳው ፡ ንጉሥ ፡
ከኢኮንያን ፡ ጋር ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ የማረከ
ውም ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆር ፡ ነው ።
፬፤ ሕልሙም ፡ ይህ ፡ ነው ፤ እነሆ ፥ ቃል ፡ ተሰማ ፥
መነዋወጥና ፡ መታወክ ፡ ተደረገ ፥ ነጐድጓድም ፡
ተሰማ ፥ በምድርም ፡ ላይ ፡ ችከላ ፡ ተደረገ ።
፭፤ እነሆም ፥ ከፍ ፡ ያሉ ፡ የተዘጋጁ ፡ ሁለት ፡ እባቦች ፡
ሊተጋገሉ ፡ መጡ ፤ ቃላቸውም ፡ ብዙ ፡ ሆነ ።
፮፤ ከቃላቸውም ፡ የተነሣ ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ከጻድ
ቃን ፡ ሕዝብ ፡ ጋር ፡ ይዋጉ ፡ ዘንድ ፡ ለሰልፍ ፡
፯፤ ተዘጋጁ ። እነሆም ፡ ጭግግና ፡ ጨለማ ፥ ኀዘ
ንና ፡ መከራ ፥ ጭንቅና ፡ ታላቅ ፡ ሁከት ፡ በም
፰፤ ድር ፡ የሚደረግበት ፡ ቀን ፡ ነበረ ፤ ጻድቃን ፡
ሕዝቦች ፡ ሁሉ ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡ እየፈሩ ፡ ታወኩ ፥
፱፤ ለጥፋትም ፡ ተዘጋጁ ፤ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡
ጮኹ ። ከጩኸታቸው ፡ የተነሣ ፡ ከትንሽ ፡
ምንጭ ፡ ብዙ ፡ ውኃ ፡ እንዳለበት ፡ እንደ ፡
፲፤ ትልቅ ፡ ወንዝ ፡ ሆነ ፤ ብርሃንና ፡ ፀሐይ ፡ ወጣ ፤
የተዋረዱም ፡ ሰዎች ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያሉ ፡ ነበሩ ፥ የከ
፲፩፤ በሩ ፡ ሰዎችንም ፡ አጠፉአቸው ። መርዶክዮ
ስም ፡ ይህን ፡ ሕልም ፡ እግዚአብሔርም ፡ ያደ
ርግ ፡ ዘንድ ፡ የቈረጠውን ፡ ነገር ፡ አይቶ ፡ ተነሣ ፥
ይህንም ፡ ነገር ፡ በልቡ ፡ አደረገ ፥ እስከ ፡ ሌሊ
ትም ፡ ድረስ ፡ በሁሉ ፡ ጐዳና ፡ ያስተውለው ፡
ዘንድ ፡ ወደደ ።
፲፪፤ መርዶክዮስም ፡ ሀገሩንና ፡ አደባባይዋን ፡
ከሚጠብቁ ፡ ከንጉሡ ፡ ባለሟሎች ፡ ከሁለቱ ፡
ከታራና ፡ ከገበታ ፡ ጋር ፡ በአደባባይ ፡ ኖረ ።
፲፫፤ ያሰቡት ፡ ምክራቸውንም ፡ ሰማ ፤ ንጉሡ ፡ አር
ጤክስስን ፡ ይገድሉት ፡ ዘንድ ፡ ወንጀልን ፡ እን
ዳዘጋጁ ፡ አወቀ ፡ ተረዳ ፤ ለንጉሡም ፡ የእነር
፲፬፤ ሱን ፡ ነገር ፡ ነገረው ። ንጉሡ ፡ ሁለቱን ፡ ሁሉ ፡
ባለሟሎቹን ፡ መረመራቸው ፡ ኃጢአታቸው
፲፭፤ ንም ፡ አምነው ፡ ተቀጡ ። ንጉሡም ፡ ይህንን ፡
ነገር ፡ ወግ ፡ ታሪክ ፡ በተጻፈበት ፡ መጽሐፍ ፡
፲፮፤ ጻፈው ፤ መርዶክዮስም ፡ ጻፈው ። ንጉሡም ፡
መርዶክዮስን ፡ ያስተምር ፡ ዘንድ ፡ አዘዘው ፡
፲፯፤ ስለዚህም ፡ ነገር ፡ ድርጎ ፡ አወጣለት ። ትው
ልዱ ፡ የአጋግ ፡ ወገን ፡ የሆነ ፡ ሐማ ፡ ግን ፡ የከ
በረ ፡ ነበረ ፡ በንጉሡም ፡ ፊት ፡ ይቆም ፡ ነበር ፤
የንጉሡ ፡ ባለሟሎች ፡ የሆኑ ፡ እለዚያ ፡ ሰዎች ፡
ስለ ፡ ሞቱ ፡ በወገኖቹና ፡ በመርዶክዮስ ፡ ክፉ ፡
ነገርን ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ ይወድድ ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

በአርጤክስስም ፡ ዘመን ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፤ ይህም ፡ ፩፤
አርጤክስስ ፡ ከህንድ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ኢትዮ
ጵያ ፡ ድረስ ፡ በመቶ ፡ ሀያ ፡ ሰባት ፡ አገሮች ፡
ላይ ፡ ነገሠ ። በዚያም ፡ ዘመን ፡ ንጉሡ ፡ አርጤ ፪፤
ክስስ ፡ በሱሳ ፡ ግንብ ፡ በነበረው ፡ በመንግሥቱ ፡
ዙፋን ፡ ላይ ፡ ተቀምጦ ፡ ሳለ ፥ በነገሠ ፡ በሦስተ ፫፤
ኛው ፡ ዓመት ፡ ለባለምዋሎቹና ፡ ለአገልጋዮቹ ፡
ሁሉ ፡ ግብዣ ፡ አደረገ ፤ የፋርስና ፡ የሜዶን ፡
ታላላቆች ፡ ሁሉ ፥ የየአገሩ ፡ አዛውንትና ፡ ሹማ
ምት ፥ በፊቱ ፡ ነበሩ ፤ የከበረውንም ፡ የመንግ ፬፤
ሥቱን ፡ ሀብት ፥ የታላቁንም ፡ የግርማዊነቱን ፡
ክብር ፡ መቶ ፡ ሰማንያ ፡ ቀን ፡ ያህል ፡ አሳያቸው ።
ይህም ፡ ቀን ፡ በተፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ በሱሳ ፡ ግንብ ፡ ፭፤
ውስጥ ፡ ለተገኙት ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ከታላቁ ፡
ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ታናሹ ፡ ድረስ ፡ ንጉሡ ፡ በን
ጉሡ ፡ ቤት ፡ አታክልት ፡ ውስጥ ፡ ባለው ፡ አደ
ባባይ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ግብዣ ፡ አደረገ ። ነጭ ፥ ፮፤
አረንጓዴ ፥ ሰማያዊም ፡ መጋረጆች ፡ ከጥሩ ፡
በፍታና ፡ ከሐምራዊ ፡ ግምጃ ፡ በተሠራ ፡ ገመድ ፥
በብር ፡ ቀለበትና ፡ በዕብነ ፡ በረድ ፡ አዕማድ ፡
ላይ ፡ ተዘርግተው ፡ ነበር ፤ አልጋዎቹም ፡ ከወ
ርቅና ፡ ከብር ፡ ተሠርተው ፡ በቀይና ፡ በነጭ ፡
በብጫና ፡ በጥቁር ፡ ዕብነ ፡ በረድ ፡ ወለል ፡ ላይ ፡
ነበሩ ። መጠጡም ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ በወርቅ ፡ ፯፤
ዕቃ ፡ ይታደል ፡ ነበር ፤ የንጉሡም ፡ የወይን ፡
ጠጅ ፡ እንደ ፡ ንጉሡ ፡ ለጋስነት ፡ መጠን ፡ እጅግ ፡
ብዙ ፡ ነበረ ። ንጉሡም ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ፰፤
ፈቃድ ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ለቤቱ ፡ አዛዦች ፡
ሁሉ ፡ አዝዞ ፡ ነበርና ፡ መጠጡ ፡ እንደ ፡ ወግ ፡
አልነበረም ። ንግሥቲቱም ፡ አስጢን ፡ በንጉሡ ፡ ፱፤
በአርጤክስስ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ለሴቶች ፡
ግብዣ ፡ አደረገች ።
በሰባተኛውም ፡ ቀን ፡ ንጉሡ ፡ አርጤክስስ ፡ ፲፤፲፩፤
የወይን ፡ ጠጅ ፡ ጠጥቶ ፡ ደስ ፡ ባለው ፡ ጊዜ ፥
ንግሥቲቱ ፡ አስጢን ፡ መልከ ፡ መልካም ፡ ነበ
ረችና ፡ ውበትዋ ፡ ለአሕዛብና ፡ ለአለቆች ፡ እን
ዲታይ ፡ የመንግሥቱን ፡ ዘውድ ፡ ጭነው ፡ ወደ ፡
ንጉሡ ፡ ፊት ፡ ያመጡአት ፡ ዘንድ ፡ በፊቱ ፡ የሚ
ያገለግሉትን ፡ ሰባቱን ፡ ጃንደረቦች ፡ ምሁማ
ንን ፥ በዛንን ፥ ሐርቦናን ፥ ገበታን ፥ ዘቶልታን ፥
ዜታርን ፥ ከርከስን ፡ አዘዛቸው ። ነገር ፡ ግን ፡ ፲፪፤
ንግሥቲቱ ፡ አስጢን ፡ በጃንደረቦቹ ፡ እጅ ፡ በላ
ከው ፡ በንጉሡ ፡ ትእዛዝ ፡ ትመጣ ፡ ዘንድ ፡
እንቢ ፡ አለች ፤ ንጉሡም ፡ እጅግ ፡ ተቈጣ ፥
በቍጣውም ፡ ተናደደ ።
ሕግንና ፡ ፍርድን ፡ በሚያውቁ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ፲፫፤
የንጉሡ ፡ ወግ ፡ እንዲህ ፡ ነበረና ፡ ንጉሡ ፡ የዘ
መኑን ፡ ነገር ፡ የሚያውቁትን ፡ ጥበበኞችን ፥

፲፬፡ በመንግሥቱም ፡ ቀዳሚዎች ፡ ሆነው ፡ የሚቀ
መጡ ፡ የንጉሡ ፡ በለምዋሎች ፡ ሰባቱ ፡ የፋ
ርስና ፡ የሚዶን ፡ መሳፍንት ፡ አርቄስዮስ ፥
ሺታር ፥ አድማታ ፥ ተርሺሽ ፥ ሚሬስ ፥ ማሌ
፲፭፡ ሴዓር ፥ ምሙካን ፡ በአጠገቡ ፡ ሳሉ ፡— በጃን
ደረቦች ፡ እጅ ፡ የተላከበትን ፡ የንጉሡን ፡ የአር
ጤክስስን ፡ ትእዛዝ ፡ ስላላደረገች ፡ በንግሥቲቱ ፡
በአስጢን ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ሕጉ ፡ የምናደርገው ፡
ምንድር ፡ ነው ? አላቸው ።
፲፮፡ ምሙካንም ፡ በንጉሡና ፡ በአዛውንቱ ፡ ፊት ፡
እንዲህ ፡ አለ ፡— ንግሥቲቱ ፡ አስጢን ፡ አዛው
ንቱን ፡ ሁሉና ፡ በንጉሡ ፡ በአርጤክስስ ፡ አገር ፡
ያሉትን ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ በድላለች ፡ እንጂ ፡
፲፯፡ ንጉሡን ፡ ብቻ ፡ የበደለች ፡ አይደለችም ። ይህ ፡
የንግሥቲቱ ፡ ነገር ፡ ወደ ፡ ሴቶች ፡ ሁሉ ፡ ይደ
ርሳልና ፡— ንጉሡ ፡ አርጤክስስ ፡ ንግሥቲቱ ፡
አስጢን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ ትገባ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፥
እርስዋ ፡ ግን ፡ አልገባችም ፡ ተብሎ ፡ በተነገረ ፡
ጊዜ ፡ ባሎቻቸው ፡ በዓይናቸው ፡ ዘንድ ፡ የተ
፲፰፡ ናቁ ፡ ይሆናሉ ። ዛሬም ፡ የንግሥቲቱን ፡ ነገር ፡
የሰሙት ፡ የፋርስና ፡ የሚዶን ፡ ወይዛዝር ፡ እን
ዲህና ፡ እንዲህ ፡ ብለው ፡ ለንጉሡ ፡ አዛውንት ፡
ሁሉ ፡ ይናገራሉ ፥ ንቀትና ፡ ቍጣም ፡ ይበዛል ።
፲፱፡ ንጉሡም ፡ ቢፈቅድ ፥ አስጢን ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡
ወደ ፡ አርጤክስስ ፡ ፊት ፡ ከእንግዲህ ፡ ወዲህ ፡
እንዳትገባ ፡ የንጉሡ ፡ ትእዛዝ ፡ ከእርሱ ፡ ይውጣ ፥
እንዳይፈርስም ፡ በፋርስና ፡ በሚዶን ፡ ሕግ ፡
ይጻፍ ፤ ንጉሡም ፡ ንግሥትነትዋን ፡ ከእርስዋ ፡
፳፡ ለተሻለችው ፡ ለሌላይቱ ፡ ይስጥ ። የንጉሡም ፡
ትእዛዝ ፡ በሰፊው ፡ መንግሥቱ ፡ ሁሉ ፡ በተነ
ገረ ፡ ጊዜ ፡ ሴቶች ፡ ሁሉ ፡ ባሎቻቸውን ፡ ታላ
፳፩፡ ቁንም ፡ ታናሹንም ፡ ያከብራሉ ። ይህም ፡
ምክር ፡ ንጉሡንና ፡ አዛውንቱን ፡ ደስ ፡ አሰኛ
ቸው ፤ ንጉሡም ፡ እንደ ፡ ምሙካን ፡ ቃል ፡ አደ
፳፪፡ ረገ ። ሰው ፡ ሁሉ ፡ በቤቱ ፡ አለቃ ፡ ይሁን ፡
በሕዝቡም ፡ ቋንቋ ፡ ይናገር ፡ ብሎ ፡ ለአገሩ ፡
ሁሉ ፡ እንደ ፡ ጽሕፈቱ ፡ ለሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡
እንደ ፡ ቋንቋው ፡ ደብዳቤዎችን ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡
አገሮች ፡ ሁሉ ፡ ሰደደ ።

ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩፡ ከዚህም ፡ ነገር ፡ በኋላ ፡ የንጉሡ ፡ የአርጤክ
ስስ ፡ ቍጣ ፡ በበረደ ፡ ጊዜ ፡ አስጢንና ፡ ያደረገ
፪፡ ችውን ፡ የፈረደባትንም ፡ ነገር ፡ አሰበ ። ንጉ
ሡንም ፡ የሚያገለግሉ ፡ ብላቴኖች ፡ እንዲህ ፡
አሉት ፡— መልከ ፡ መልካም ፡ የሆኑ ፡ ደናግል ፡
፫፡ ለንጉሡ ፡ ይፈለጉለት ፤ ሴቶችን ፡ ከሚጠብቅ ፡
ከንጉሡ ፡ ጃንደረባ ፡ ከሄጌ ፡ እጅ ፡ በታች ፡
እንዲያደርጓቸው ፡ መልከ ፡ መልካሞቹን ፡ ደና
ግል ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ሱሳ ፡ ግንብ ፡ ወደ ፡ ሴቶች ፡
ቤት ፡ ይሰበስቡአቸው ፡ ዘንድ ፡ ንጉሡ ፡ በመ
ንግሥቱ ፡ አገሮች ፡ ሁሉ ፡ ሹማምቶችን ፡ ያኑር ፤
ቅባትና ፡ የሚያስፈልጋቸውም ፡ ይሰጣቸው ፤
፬፡ ንጉሡንም ፡ ደስ ፡ የምታሰኝ ፡ ቆንጆ ፡ በአስ
ጢን ፡ ስፍራ ፡ ትንገሥ ። ይህም ፡ ነገር ፡ ንጉ
ሡን ፡ ደስ ፡ አሰኘው ፥ እንዲሁም ፡ አደረገ ።
አንድ ፡ አይሁዳዊ ፡ የቂስ ፡ ልጅ ፡ የሰሚኢ ፡ ፭፡
ልጅ ፡ የኢያዕር ፡ ልጅ ፡ መርዶክዮስ ፡ የሚባል ፡
ብንያማዊ ፡ በሱሳ ፡ ግንብ ፡ ነበረ ። እርሱም ፡ ፮፡
የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ናቡከደነፆር ፡ ከማረካቸው ፡
ከይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ከኢኮንያን ፡ ጋር ፡ ከተማረ
ኩት ፡ ምርኮኞች ፡ ጋር ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ የተማ
ረከ ፡ ነበረ ። አባትና ፡ እናትም ፡ አልነበሩ ፡ት ፡ ፯፡
ምና ፡ የአጎቱ ፡ ልጅ ፡ ሀደሳ ፡ የተባለችውን ፡
አስቴርን ፤ አሳድጎ ፡ ነበር ፤ ቆንጆይቱም ፡ የተ
ዋበችና ፡ መልከ ፡ መልካም ፡ ነበረች ፤ አባት
ዋና ፡ እናትዋም ፡ ከሞቱ ፡ በኋላ ፡ መርዶክዮስ ፡
እንደ ፡ ልጁ ፡ አድርጎ ፡ ወስዶአት ፡ ነበር ።
የንጉሡም ፡ ትእዛዝና ፡ አዋጅ ፡ በተሰማ ፡ ፰፡
ጊዜ ፥ ብዙም ፡ ቈነጃጅት ፡ ወደ ፡ ሱሳ ፡ ግንብ ፡
ወደ ፡ ሄጌ ፡ እጅ ፡ በተሰበሰቡ ፡ ጊዜ ፥ አስቴር ፡
ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ቤት ፡ ወደ ፡ ሴቶች ፡ ጠባ
ቂው ፡ ወደ ፡ ሄጌ ፡ ተወሰደች ። ቆንጆይቱም ፡ ፱፡
ደስ ፡ አሰኘችው ፥ በእርሱም ፡ ዘንድ ፡ ሞገስ ፡
አገኘች ፤ ቅባትዋንም ፡ ድርሻዋንም ፡ ከንጉ
ሡም ፡ ቤት ፡ ልታገኝ ፡ የሚገባትን ፡ ሰባት ፡
ደንገጥሮች ፡ ፈጥኖ ፡ ሰጣት ፤ እርስዋንና ፡ ደን
ገጥሮችዋንም ፡ በሴቶች ፡ ቤት ፡ በተመረጠ ፡
ስፍራ ፡ አኖረ ። ይህንም ፡ እንዳትናገር ፡ መር ፲፡
ዶክዮስ ፡ አገዘአት ፡ ነበርና ፡ አስቴር ፡ ሕዝብ
ዋንና ፡ ወገንዋን ፡ አልተናገረችም ። መርዶክ ፲፩፡
ዮስም ፡ የአስቴርን ፡ ደኅንነትና ፡ የሚሆንላትን ፡
ያውቅ ፡ ዘንድ ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ በሴቶች ፡ ቤት ፡
ወለል ፡ ትይዩ ፡ ይመላለስ ፡ ነበር ።
የመንጻታቸውም ፡ ወራት ፡ ስድስት ፡ ወር ፡ ፲፪፡
ያህል ፡ በከርቤ ፡ ዘይት ፥ ስድስት ፡ ወርም ፡ በጣ
ፋጭ ፡ ሽቱና ፡ በልዩ ፡ ልዩም ፡ በሚያነጻ ፡ ነገር ፡
ይፈጸም ፡ ነበርና ፡ እንደ ፡ ሴቶች ፡ ወግ ፡ አሥራ ፡
ሁለት ፡ ወር ፡ እንዲሁ ፡ ከተደረገላት ፡ በኋላ ፡
ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወደ ፡ አርጤክስስ ፡ ለመግባት ፡
የአንዳንዲቱ ፡ ቆንጆ ፡ ተራ ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፥
በዚህ ፡ ወግ ፡ ቆንጆይቱ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ትገባ ፡ ፲፫፡
ነበር ፤ ከሴቶች ፡ ቤት ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ቤት ፡ ለመ
ውሰድ ፡ የምትሺውን ፡ ሁሉ ፡ ይሰጡአት ፡ ነበር ።
ማታም ፡ ትገባ ፡ ነበር ፥ ሲነጋም ፡ ተመልሳ ፡ ፲፬፡
ወደ ፡ ሁለተኛው ፡ ሴቶች ፡ ቤት ፡ ቁባቶችን ፡
ወደሚጠብቅ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ጃንደረባ ፡ ወደ ፡
ጋይ ፡ ትመጣ ፡ ነበር ፤ ንጉሡም ፡ ያልፈለጋት ፡
እንደ ፡ ሆነ ፥ በስምዋም ፡ ያልተጠራች ፡ እንደ ፡
ሆነ ፥ ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ አት
ገባም ፡ ነበር ። ወደ ፡ ንጉሡም ፡ ትገባ ፡ ፲፭፡
ዘንድ ፡ የመርዶክዮስ ፡ አጎት ፡ የአቢካኢል ፡
ልጅ ፡ የአስቴር ፡ ተራ ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ የሴቶች ፡
ጠባቂው ፡ የንጉሡ ፡ ጃንደረባ ፡ ሄጌ ፡ ከሚለው ፡
በቀር ፡ ምንም ፡ አልፈለገችም ፡ ነበር ፤ አስቴ
ርም ፡ በሚያዩአት ፡ ሁሉ ፡ ዓይን ፡ ሞገስ ፡ አግ
ኝታ ፡ ነበርና ።
አርጤክስስም ፡ በነገሠ ፡ በሰባተኛው ፡ ዓመት ፡ ፲፮፡

አዳር ፡ በሚባለው ፡ በአሥራ ፡ ሁለተኛው ፡
ወር ፡ አስቴር ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ቤት ፡ ተወሰደች ።
፲፯፤ ንጉሡም ፡ ከሴቶች ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ አስቴርን ፡
ወደደ ፥ በዓይኑም ፡ ከደናግል ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡
ሞገስንና ፡ መወደድን ፡ አገኘች ፤ የመንግሥቱ
ንም ፡ ዘውድ ፡ በራስዋ ፡ ላይ ፡ አደረገ ፥ በአስ
፲፰፤ ጢንም ፡ ፋንታ ፡ አነገሣት ። ንጉሡም ፡ ስለ ፡ አስ
ቴር ፡ ለባለምዋሎቹና ፡ ለአገልጋዮቹ ፡ ሁሉ ፡
ሰባት ፡ ቀን ፡ ያህል ፡ ትልቅ ፡ ግብዣ ፡ አደረገ ፤
ለአገሮቹም ፡ ሁሉ ፡ ይቅርታ ፡ አደረገ ፥ እንደ ፡
ንጉሡም ፡ ለጋስነት ፡ መጠን ፡ ስጦታ ፡ ሰጠ ።
፲፱፤ ደናግሉም ፡ ዳግመኛ ፡ በተሰበሰቡ ፡ ጊዜ ፡
መርዶክዮስ ፡ በንጉሡ ፡ በር ፡ ይቀመጥ ፡ ነበር ።
፳፤ አስቴርም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ እንዳደገችበት ፡
ጊዜ ፡ የመርዶክዮስን ፡ ትእዛዝ ፡ ታደርግ ፡ ነበ
ርና ፡ መርዶክዮስ ፡ እንዳዘዛት ፡ አስቴር ፡ ወገ
፳፩፤ ንዋንና ፡ ሕዝብዋን ፡ አልተናገረችም ። በዚ
ያም ፡ ወራት ፡ መርዶክዮስ ፡ በንጉሡ ፡ በር ፡
ተቀምጦ ፡ ሳለ ፡ ደጁን ፡ ከሚጠብቁት ፡ ከን
ጉሡ ፡ ጃንደረቦች ፡ ሁለቱ ፡ ገበታና ፡ ታራ ፡
ተቈጡ ፥ እጃቸውንም ፡ በንጉሡ ፡ በአርጤክ
፳፪፤ ስስ ፡ ላይ ፡ ያነሡ ፡ ዘንድ ፡ ፈለጉ ። ነገሩም ፡ ለመ
ርዶክዮስ ፡ ተገለጠ ፥ እርሱም ፡ ለንግሥቲቱ ፡
ለአስቴር ፡ ነገራት ፤ አስቴርም ፡ በመርዶክዮስ ፡
፳፫፤ ስም ፡ ለንጉሡ ፡ ነገረች ። ነገሩም ፡ ተመረመረ ፥
እንዲህም ፡ ሆኖ ፡ ተገኘ ፥ ሁለቱም ፡ በዛፍ ፡
ላይ ፡ ተሰቀሉ ፤ ያም ፡ በንጉሡ ፡ ፊት ፡ በታሪክ ፡
መጽሐፍ ፡ ተጻፈ ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩፤ ከዚህም ፡ ነገር ፡ በኋላ ፡ ንጉሡ ፡ አርጤክስስ ፡
የአጋጋዊውን ፡ የሐመዳቱን ፡ ልጅ ፡ ሐማን ፡
ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረገው ፥ አከበረውም ፥ ወንበ
ሩንም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ከነበሩት ፡ አዛውንት ፡
፪፤ ሁሉ ፡ በላይ ፡ አደረገለት ። ንጉሡም ፡ ስለ ፡
እርሱ ፡ እንዲሁ ፡ አገዘዘ ፡ ነበርና ፡ በንጉሡ ፡
በር ፡ ያሉት ፡ የንጉሡ ፡ ባሪያዎች ፡ ሁሉ ፡ ተደ
ፍተው ፡ ለሐማ ፡ ይሰግዱ ፡ ነበር ። መርዶክዮስ ፡
፫፤ ግን ፡ አልተደፋም ፥ አልሰገደለትም ። በንጉ
ሡም ፡ በር ፡ ያሉት ፡ የንጉሡ ፡ ባሪያዎች ፡ መር
ዶክዮስን ፦ የንጉሡን ፡ ትእዛዝ ፡ ለምን ፡ ትተ
፬፤ ላለፋለህ ? አሉት ። ይህንም ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡
እየተናገሩ ፡ እርሱ ፡ ባልሰማቸው ፡ ጊዜ ፡ አይ
ሁዳዊ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ነግሮአቸው ፡ ነበርና ፡ የመ
ርዶክዮስ ፡ ነገር ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ያዩ ፡
፭፤ ዘንድ ፡ ለሐማ ፡ ነገሩት ። ሐማም ፡ መርዶክዮስ ፡
እንዳልተደፋለት ፡ እንዳልሰገደለትም ፡ ባየ ፡
፮፤ ጊዜ ፡ እጅግ ፡ ተቈጣ ። የመርዶክዮስን ፡ ወገን ፡
ነግረውት ፡ ነበርና ፡ በመርዶክዮስ ፡ ብቻ ፡ እጁን ፡
ይጭን ፡ ዘንድ ፡ በዓይኑ ፡ ተናቀ ፤ ሐማም ፡ በአር
ጤክስስ ፡ መንግሥት ፡ ሁሉ ፡ የነበሩትን ፡ የመ
ርዶክዮስን ፡ ሕዝብ ፡ አይሁድን ፡ ሁሉ ፡ ሊያ
ጠፉ ፡ ፈለገ ።
፯፤ በንጉሡም ፡ በአርጤክስስ ፡ በአሥራ ፡ ሁለ
ተኛው ፡ ዓመት ፡ ከመጀመሪያው ፡ ወር ፡ ከኒሳን ፡
ጀምሮ ፡ በየዕለቱና ፡ በየወሩ ፡ እስከ ፡ አሥራ ፡
ሁለተኛው ፡ ወር ፡ እስከ ፡ አዳር ፡ ድረስ ፡ በሐማ ፡
ፊት ፡ ፉር ፡ የተባለውን ፡ ዕጣ ፡ ይጥሉ ፡ ነበር ።
ሐማም ፡ ንጉሡን ፡ አርጤክስስን ፦ አንድ ፡ ፰፤
ሕዝብ ፡ በአሕዛብ ፡ መካከል ፡ በመንግሥትህ ፡
አገሮች ፡ ሁሉ ፡ ተበትነዋል ፤ ሕጋቸውም ፡ ከሕ
ዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ሕግ ፡ የተለየ ፡ ነው ፥ የንጉሡንም ፡
ሕግ ፡ አይጠብቁም ፤ ንጉሡም ፡ ይተዋቸው ፡
ዘንድ ፡ አይገባውም ። ንጉሡም ፡ ቢፈቅድ ፡ ፱፤
እንዲጠፉ ፡ ይጻፍ ፤ እኔም ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡
ግምጃ ፡ ቤት ፡ ያገቡት ፡ ዘንድ ፡ አሥር ፡ ሺህ ፡
መክሊት ፡ ብር ፡ የንጉሡን ፡ ሥራ ፡ በሚሠሩት ፡
እጅ ፡ እመዝናለሁ ፡ አለው ። ንጉሡም ፡ ቀለበ ፲፤
ቱን ፡ ከእጁ ፡ አወለቀ ፥ ለአይሁድም ፡ ጠላት ፡
ለአጋጋዊው ፡ ለሐመዳቱ ፡ ልጅ ፡ ለሐማ ፡ ሰጠው ።
ንጉሡም ፡ ሐማን ፦ ደስ ፡ የሚያሰኝህን ፡ ፲፩፤
ነገር ፡ ታደርግባቸው ፡ ዘንድ ፡ ብሩም ፡ ሕዝ
ቡም ፡ ለአንተ ፡ ተሰጥቶሃል ፡ አለው ።
በመጀመሪያውም ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በአሥራ ፡ ፲፪፤
ሦስተኛው ፡ ቀን ፡ የንጉሡ ፡ ጸሐፊዎች ፡ ተጠሩ ፤
ከህንድ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ድረስ ፡
ወዳሉ ፡ መቶ ፡ ሀያ ፡ ሰባት ፡ አገሮች ፥ በየአገሩ ፡
ወዳሉ ፡ ሹማምትና ፡ አለቆች ፡ ወደ ፡ አሕዛብም ፡
ሁሉ ፡ ገዢዎች ፡ እንደ ፡ ቋንቋቸው ፡ በንጉሡ ፡
በአርጤክስስ ፡ ቃል ፡ ሐማ ፡ እንዳዘዘ ፡ ተጻፈ ፥
በንጉሡም ፡ ቀለበት ፡ ታተመ ። በአሥራ ፡ ሁለ ፲፫፤
ተኛው ፡ ወር ፡ በአዳር ፡ በአሥራ ፡ ሦስተኛው ፡
ቀን ፡ አይሁድን ፡ ሁሉ ፥ ልጆችንና ፡ ሽማግሌ
ዎችን ፥ ሕፃናቶችንና ፡ ሴቶችን ፥ በአንድ ፡
ቀን ፡ ያጠፉና ፡ ይገድሉ ፡ ዘንድ ፥ ይደመስሱም ፡
ዘንድ ፥ ምርኮአቸውንም ፡ ይዘርፉ ፡ ዘንድ ፡ ደብ
ዳቤዎች ፡ በመልእክተኞች ፡ እጅ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡
አገሮች ፡ ሁሉ ፡ ተላኩ ።
የንጉሡ ፡ የአርጤክስስ ፡ ደብዳቤዎች ፡ እን (፩)
ዲህ ፡ ይላሉ ። ከህንድ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ኢትዮ
ጵያ ፡ ድረስ ፡ በመቶ ፡ ሀያ ፡ ሰባት ፡ አገሮች ፡ ላሉ ፡
ለደጃዝማቾችና ፡ ለራሶች ፡ ለመኳንንትም ፡ ትድ
ረስ ፡ ይላሉ ። እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ጻፈ ፦ ብዙ ፡ (፪)
አሕዛብን ፡ ከገዛሁ ፡ በኋላ ፤ አገሩንም ፡ ሁሉ ፡
ከገዛሁ ፡ በኋላ ፡ እነዚህን ፡ አጥፍቼ ፡ ሁሉን ፡
አዘጋጅቼ ፡ ለዘላለሙ ፡ በየዋሃት ፡ በጸጥታ ፡
እኖር ፡ ዘንድ ፡ ወደድሁ ። መንግሥቱ ፡ የተወ
ደደ ፡ ጸጥ ፡ ያለ ፡ እንደ ፡ መሆኑ ፡ ሁሉን ፡ ሠራ
ርቼ ፡ ለኔ ፡ የሚታዘዝልኝ ፡ ሁሉ ፡ ያለ ፡ ድንጋጤ ፡
ይኖር ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ራሴን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡
የማደርግ ፡ በመንግሥቴ ፡ ጽናት ፡ አይደለም ፤
ደብዳቤይቱም ፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡
ትድረስ ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ የሚገኝ ፡ በሕዝቡም ፡
ዘንድ ፡ የሚወደድ ፡ ተድላ ፡ ደስታን ፡ አደርጋ
ለሁ ፡ አለ ። በሚገባ ፡ ሁለጊዜ ፡ ይህንን ፡ ማዘ (፫)
ጋጀት ፡ በምችል ፡ ገንዘብ ፡ ለመክሮች ፡ እሺ ፡
ብዬ ፡ በልቡናዬ ፡ ሳልጸጸት ፡ በጎ ፡ ነገርን ፡ አደ
ርግ ፡ ዘንድ ፡ መጣሁ ። ከእኔ ፡ በታች ፡ ከተሾመ ፡

ወደ ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ ከመራን ፡ ሥርዓቱም ፡ ልዩ ፡
የሆነ ፡ ከሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ተለይቶ ፡ ለንጉሡ ፡
ትእዛዝ ፡ ሁልጊዜ ፡ የማይታዘዝ ፡ ሕጋችንና ፡
ሥርዓታችንንም ፡ እንቢ ፡ የሚል ፡ እስራኤል ፡
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሁሉ ፡ ከሉ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡
ጋር ፡ አንድ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ከነገረን ፡ ከሐማ ፡ በእ
(፩) ውነት ፡ በሚገባ ፡ ተላከ ። ይህንንም ፡ ወገን ፡
ብቻውን ፡ ተለይቶ ፡ ሥርዓቱም ፡ ከሰው ፡ ሥር
ዓት ፡ የተለየ ፡ ሆኖ ፡ በዕድ ፡ ሆኖ ፡ ተለውጦ ፡
ከሕጋችንም ፡ ወጥቶ ፡ አገኘነው ። ፈቃዳቸው
ንም ፡ ለመፈጸም ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ ይሠራሉ ፥ መን
ግሥታችንንም ፡ እንደ ፡ ኢምንት ፡ አደረጓት ።
(፪) በሁሉ ፡ ላይ ፡ በተሾመ ፡ ከአባታችን ፡ በታች ፡
በሆነ ፡ በሐማ ፡ ደብዳቤዎች ፡ ስለ ፡ ጻፍንላችሁ ፥
ፈጽማችሁ ፡ ሳትራሩላቸው ፡ በዚች ፡ ዓመት ፡
አዳር ፡ በበተ ፡ በአሥራ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡
ሁሉንም ፡ በጠላታቸው ፡ ሰይፍ ፡ ከልጆቻቸ
ውና ፡ ከሚስቶቻቸው ፡ ጋር ፡ ያጠፉአቸው ፡
(፫) ዘንድ ፡ እነሆ ፡ አዘዝን ። እንደዚሁ ፡ ታናናሹን ፡
ታላላቁንም ፡ በአንዲት ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡
ታወርዱአቸው ፡ ዘንድ ፡ እነሆ ፡ አዘዝን ፤ ከዚህ ፡
በኋላ ፡ አገራችን ፡ ፈጽማ ፡ ከሥራቸው ፡ ታርፍ ፡
ዘንድ ፡ ከእነርሱ ፡ የምታስቀሩት ፡ አይኑር ።
፲፬፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ ይዘጋጁ ፡ ዘንድ ፡ የደብዳቤው ፡
ቅጅ ፡ በየአገሩ ፡ ላሉ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ታወጀ ።
፲፭፤ መልእክተኞቹም ፡ በንጉሡ ፡ ትእዛዝ ፡ እየቸ
ኰሉ ፡ ሄዱ ፥ አዋጁም ፡ በሱሳ ፡ ግንብ ፡ ተነ
ገረ ። ንጉሡና ፡ ሐማ ፡ ሊጠጡ ፡ ተቀመጡ ፤
ከተማይቱ ፡ ሱሳ ፡ ግን ፡ ተደናገጠች ።

ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩፤ መርዶክዮስም ፡ የተደረገውን ፡ ሁሉ ፡ በወቀ ፡
ጊዜ ፡ ልብሱን ፡ ቀደደ ፥ ማቅም ፡ ለበሰ ፡ አመ
ድም ፡ ነሰነሰ ፥ ወደ ፡ ከተማይቱም ፡ መካከል ፡
ወጣ ፥ ታላቅም ፡ የመረረ ፡ ጩኸት ፡ ጮኸ ።
፪፤ ማቅም ፡ ለብሶ ፡ በንጉሥ ፡ በር ፡ መግባት ፡ አይ
ገባም ፡ ነበርና ፡ እስከ ፡ ንጉሡ ፡ በር ፡ አቅራ
፫፤ ቢያ ፡ መጣ ። የንጉሡም ፡ ትእዛዝና ፡ አዋጅ ፡
በደረሰበት ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ በአይሁድ ፡ ላይ ፡
ታላቅ ፡ ኀዘንና ፡ ጾም ፡ ልቅሶና ፡ ዋይታም ፡ ሆነ ፡
ብዙዎችም ፡ ማቅና ፡ አመድ ፡ አነጠፉ ።
፬፤ የአስቴርም ፡ ደንገጥሮችዋና ፡ ጃንደረቦችዋ ፡
መጥተው ፡ ነገሩአት ፥ ንግሥቲቱም ፡ እጅግ ፡
አዘነች ፤ ማቁንም ፡ ለውጦ ፡ ልብስ ፡ ይለብስ ፡
ዘንድ ፡ ለመርዶክዮስ ፡ ሰደደችለት ፤ እርሱ ፡
፭፤ ግን ፡ አልተቀበለም ። አስቴርም ፡ ያገለግላት ፡
ዘንድ ፡ ንጉሡ ፡ ያቆመውን ፡ አክራትዮስን ፡
ጠራች ፡ እርሱም ፡ ከጃንደረቦች ፡ አንዱ ፡ ነበረ ፥
እርስዋም ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ ምንና ፡ ምን ፡ እንደ ፡
ሆነ ፡ ያስታውቃት ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ መርዶክዮስ ፡
፮፤ እንዲሄድ ፡ አዘዘችው ። አክራትዮስም ፡ በን
ጉሥ ፡ በር ፡ ፊት ፡ ወደ ፡ ነበረችው ፡ ወደ ፡ ከተ
ማይቱ ፡ አደባባይ ፡ ወደ ፡ መርዶክዮስ ፡ ወጣ ።
፯፤ መርዶክዮስም ፡ የተደረገውን ፡ ሁሉ ፥ አይሁ
ድንም ፡ ለማጥፋት ፡ ሐማ ፡ በንጉሡ ፡ ግምጃ ፡
ቤት ፡ ይመዝን ፡ ዘንድ ፡ የተናገረውን ፡ የብሩን ፡
ቍጥር ፡ ነገረው ። ለአስቴርም ፡ እንዲያሳያት ፡ ፰፤
ለመጥፋታቸው ፡ በሱሳ ፡ የተነገረውን ፡ የአዋ
ጁን ፡ ጽሕፈት ፡ ቅጅ ፡ ሰጠው ፤ ወደ ፡ ንጉሡም ፡
ገብታ ፡ ስለ ፡ ሕዝብዋ ፡ ትለምነውና ፡ ትማል
ደው ፡ ዘንድ ፡ እንዲነግራትና ፡ እንዲያዝዛት ፡
ነገረው ።
አክራትዮስም ፡ መጥቶ ፡ የመርዶክዮስን ፡ ፱፤
ቃል ፡ ለአስቴር ፡ ነገራት ። አስቴርም ፡ አክራ ፲፤
ትዮስን ፡ ተናገረችው ፥ ለመርዶክዮስም ፡ እን
ዲህ ፡ የሚል ፡ መልእክት ፡ ሰጠችው ፦ የን ፲፩፤
ጉሡ ፡ ባሪያዎችና ፡ በአገሮችም ፡ የሚኖሩ ፡
ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ወንድ ፡ ወይም ፡ ሴት ፡ ቢሆን ፡
ሳይጠራ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ውስጠኛው ፡
ወለል ፡ የሚገባ ፡ ሁሉ ፥ በሕይወት ፡ ይኖር ፡
ዘንድ ፡ ንጉሡ ፡ የወርቁን ፡ ዘንግ ፡ ከልዘረጋለት ፡
በቀር ፥ እርሱ ፡ ይሞት ፡ ዘንድ ፡ ሕግ ፡ እንዳለ ፡
ያውቃሉ ፤ እኔ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ለመግ
ባት ፡ ይህን ፡ ሠላሳውን ፡ ቀን ፡ አልተጠራሁም ።
አክራትዮስም ፡ የአስቴርን ፡ ቃል ፡ ለመርዶክ ፲፪፤
ዮስ ፡ ነገረው ።
መርዶክዮስም ፡ አክራትዮስን ፦ ሂድና ፡ ለአ ፲፫፤
ስቴር ፡ እንዲህ ፡ በላት ፡ አለው ፦ አንቺ ፦ በን
ጉሥ ፡ ቤት ፡ ስለ ፡ ሆንሁ ፡ ከአይሁድ ፡ ሁሉ ፡
ይልቅ ፡ እድናለሁ ፡ ብለሽ ፡ በልብሽ ፡ አታስቢ ።
በዚህ ፡ ጊዜ ፡ ቸል ፡ ብትዪ ፡ ዕረፍትና ፡ መዳን ፡ ፲፬፤
ለአይሁድ ፡ ከሌላ ፡ ስፍራ ፡ ይሆንላቸዋል ፥ አን
ቺና ፡ የአባትሽ ፡ ቤት ፡ ግን ፡ ትጠፋላችሁ ፤
ደግሞስ ፡ ወደ ፡ መንግሥት ፡ የመጣሽው ፡ እን
ደዚህ ፡ ላለው ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ማን ፡ ያው
ቃል ? አስቴርም ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ለመርዶክ ፲፭፤
ዮስ ፡ እንዲመልስ ፡ አዘዘችው ፦ ሄደህ ፡ በሱሳ ፡ ፲፮፤
ያሉትን ፡ አይሁድ ፡ ሁሉ ፡ ሰብስብ ፥ ለእኔም ፡
ጹሙ ፤ ሦስት ፡ ቀን ፡ ሌሊቱንና ፡ ቀኑን ፡ አትብ
ሉም ፥ አትጠጡም ፤ እኔና ፡ ደንገጥሮቼ ፡ ደግሞ ፡
እንዲሁ ፡ እንጾማለን ፤ ምንም ፡ እንኳ ፡ ያለ ፡
ሕግ ፡ ቢሆን ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ እገባለሁ ፤ ብጠ
ፋም ፡ እጠፋለሁ ። መርዶክዮስም ፡ ሄዶ ፡ አስ ፲፯፤
ቴር ፡ እንዳዘዘችው ፡ ሁሉ ፡ አደረገ ።
እግዚአብሔር ፡ ያደረገውን ፡ ሁሉ ፡ እያሰበ ፡ ፲፰፤
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለመነ ። አቤቱ ፥ አቤቱ ፥ ፲፱፤
ሁሉን ፡ የምትገዛ ፡ በሥልጣንህ ፡ ሁሉን ፡ የፈጠ
ርህ ፡ ንጉሥ ፥ እስራኤልን ፡ ታድናቸው ፡ ዘንድ ፡
ብትወድ ፡ የሚከራከርህ ፡ የሌለ ፤ ምድርና ፡ ፳፤
ሰማይን ፡ በሰማይ ፡ በታች ፡ ያለ ፡ ድንቅ ፡ ፍጥ
ረትንም ፡ ሁሉ ፡ አንተ ፡ ፈጥረሃልና ፤ የሁሉ ፡ ፳፩፤
ፈጣሪ ፡ አንተ ፡ ነህ ፡ የሚከራከርህም ፡ የሌለ ፡
ጌታ ፡ አንተ ፡ ነህ ። ከመናቅ ፡ እንዳይደለ ፡ በትዕ ፳፪፤
ቢትም ፡ እንዳይደለ ፡ አላዋቂ ፡ ስሆን ፡ ለሐማ ፡
እንዳልሰግድ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ይህንን ፡ ያደረግ
ሁት ፡ ራሴን ፡ በማኩራትም ፡ እንዳይደለ ፥
አቤቱ ፥ ሁሉን ፡ አንተ ፡ ታውቃለህ ። የእግ ፳፫፤
ዚአብሔርን ፡ ክብር ፡ የሰው ፡ ክብር ፡ እንዳላደ

ርግ፡ካንተም፡ከጌታዬ፡በቀር፡ለማንም፡እንዳ
፳፬፤ ልሰግድ ። ይህንን፡ነገር፡አደረግሁት፡እንጂ፡
እስራኤልስ፡የሚድኑ፡ከሆነ፡እግሩን፡እስም፡
ዘንድ ፡ በወደድሁ ፡ ነበር ፤ ይኸንን ፡ ሥራ ፡
፳፭፤ በትዕቢት፡አላደረግሁትም ። በጠላትነት፡ተነ
ሥተውብናልና ፡ መጀመሪያ ፡ ርስትህ ፡ እስራ
ኤልንም ፡ ያጠፉ ፡ ዘንድ ፡ ወድዶአልና ፡ አሁ
ንም ፡ አቤቱ ፡ ገዢ ፡ ንጉሥ ፡ የምትሆን ፡ የአብ
ርሃም ፡ ፈጣሪ ፡ ወገኖችህን ፡ ይቅር ፡ በል ።
፳፮፤ ማደሪያ ፡ ሊሆንህ ፡ ከግብጽ ፡ አገር ፡ ያዳንኻ
ቸው ፡ እድሎችህ ፡ እስራኤልን ፡ ቸል ፡ አት
፳፯፤ በል ። ልመናችንንም፡ሰምተህ፡ወገኖችህን፡
ይቅር፡በል ፤ አቤቱ ÷ በሕይወት፡ሳለን፡ስም
ህን፡እናመሰግን ፡ ዘንድ ፡ ኃዘናችንን ፡ ወደ ፡
ተድላ፡ደስታ፡መልሰው፡ተስፋ፡የሚያደርጉ
ህንም፡ሰዎች፡አለኝታቸውን፡አታጥፋ፡አለ ።
፳፰፤ በፊታቸው፡ሞት፡ደርሶባቸዋልና፡እስራኤል፡
ሁሉ ፡ ጮሁ ፡ ቃላቸውን ፡ አሰምተው ፡ በኃይ
ላቸው ፡ ተናገሩ ።
፳፱፤ ሞትን ፡ ወደ ፡ መፍራት ፡ ደርሳለችና ፡ አስቴ
ርም ፡ ሰውነትዋን ፡ በእግዚአብሔር ፡ አስጠበ
፴፤ ቀች ። የተድላ ፡ የደስታ ፡ ልብስዋን ፡ አው
ልቃ ፡ የልቅሶና ፡ የኃዘንን ፡ ልብስ ፡ ለበሰች ፤
የተድላ ፡ የደስታ ፡ ሽቱም ፡ ትቀባ ፡ ስለ ፡ ነበር ፡
ፋንታ ፡ በራስዋ ፡ ላይ ፡ አመድና ፡ ትቢያን ፡ ነሰ
ነሰች ፤ ሰውነትዋንም ፡ ፈጽማ ፡ አሳዘነች ÷ በጠ
ጕርዋ ፡ ሰርሜድ ፡ ጌጥ ፡ በታም ፡ ትቢያ ፡ ነሰነ
፴፩፤ ፴፪፤ ሰች ። አቤቱ ÷ ረዳት ፡ አንተ ፡ ብቻ ፡ ነህ ፤ በአ
ንተ ፡ ቃል ፡ ሞት ፡ ደርሶብኛልና ፡ ረዳት ፡ የሌ
ለኝ ፡ ብቸኛ ፡ የሆንሁ ፡ እኔን ፡ እርዳኝ ፡ ብላ ፡
ወደ ፡ እስራኤል ፡ ፈጣሪ ፡ ወደ ፡ እግዚአብ
፴፫፤ ሔር ፡ ለመነች ። እኔም ፡ ከልጅነቴ ፡ጀምሬ ፡
ከባቶቼ ፡ ወገኖች ፡ ዘንድ ÷ አቤቱ ÷ አንተ ፡ ከአ
ሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ለይተህ ፡ እስራኤልን ፡ ገንዘብ ፡
እንዳደረግሃቸው ፡ ለዘላለሙ ፡ ርስት ፡ ይሆኑህ ፡
ዘንድ ፡ አባቶቻችንንም ፡ ከዘመዶቻቸው ፡ ለይ
ተህ ፡ እንዳደረግሃቸው ፡ ሰማሁ ፡ አሁንም ፡
እንደ ፡ ተናገርህ ፡ ሁሉን ፡ አደረግህላቸው ።
፴፬፤ በፊትህ ፡ በደልን ÷ የአሕዛብን ፡ ጣዖቶች ፡ አመ
ስግነናልና ፡ በጠላቶቻችን ፡ እጅ ፡ ጣልኸን ።
፴፭፤ አቤቱ ፡ አንተ ፡ ቸር ፡ ነህ ። እጃቸውን ፡ በጣዖ
ቶቻቸው ፡ ላይ ፡ ያነሡ ፡ አሕዛብ ፡ በጽኑ ፡ አገ
ዛዝ ፡ ገዙን ፡ እንጂ ፡ አሁንም ፡ አልተዉንም ።
፴፮፤ በፍህ ፡ የሠራኸውን ፡ ሥርዓት ፡ ማደሪያህ ፡ እስ
ራኤልንም ፡ ያጠፉ ፡ ዘንድ ፡ የሚያመሰግኑህ ፡
ሰዎችንም ፡ አፋቸውን ፡ ይዘጉ ፡ ዘንድ ፡ የማደ
ሪያህ ፡ ቤተ ፡ መቅደስንም ፡ ሥርዓት ፡ መሠዊ
፴፯፤ ያህንም ፡ ያጠፉ ፡ ዘንድ ። ለከንቱ ፡ ጣዖት ፡
ለማድላት ፡ የአሕዛብንም ፡ አፍ ፡ ይከፍቱ ፡
ዘንድ ፡ ሥጋዊ ፡ ንጉሥንም ፡ ለዘላለሙ ፡ ያመሰ
ግኑ ፡ ዘንድ ፡ እጃቸውን ፡ በጣዖቱ ፡ ላይ ፡ ያነሡ ፡
አሕዛብ ፡ ጽኑ ፡ አገዛዝ ፡ ገዙን ፡ እንጂ ፡ አሁ
፴፰፤ ንም ፡ አልተዉንም ። ባጸናኸው ፡ ሕግ ፡ ያሉ ፡
እስራኤልንም ፡ አሳልፈህ ፡ ለአሕዛብ ፡ አትስጣ

ቸው ፡ ምክራቸውን ፡ ራሳቸውን ፡ ወደ ፡ ማጥ
ፋት ፡ መልሳት ፡ እንጂ ፡ በጠላትነት ፡ የተነሣ
ብን ፡ ሐማን ፡ አጕስቀሰው ፡ እንጂ ፡ በመከራ
ችን ፡ ጊዜ ፡ አይሳቁብን ። አቤቱ ፡ በመከራ ፴፱፤
ችን ፡ ጊዜ ፡ አስበን ÷ ፍጥረቱን ፡ ሁሉ ፡ ያጸናህ ፡
ንጉሥ ፡ ፈጣሪ ፡ የምትሆን ፡ አንተ ÷ እኔንም ፡
አጽናኝ ። በንጉሥ ፡ ፊት ፡ በአንደበቴ ፡ በጎ ፡ ፵፤
ነገርን ፡ እንድናገር ፡ አድርገኝ ÷ ፈጽሞ ፡ የተ
ጣላን ፡ ሐማንም ፡ ይጣላው ፡ ዘንድ ÷ ከእርሱ ፡
ጋር ፡ አንድ ፡ የሆኑ ፡ አሕዛብንም ፡ ይጠላቸው ፡
ዘንድ ÷ ልቡናውንም ፡ ሐማን ፡ ወደ ፡ መጥላት ፡
መልሰው ። እኛን ፡ ግን ፡ በሥልጣንህ ፡ አድ ፵፩፤
ነን ፡ አቤቱ ፤ ያለ ፡ አንተ ፡ ማንም ፡ ማን ፡ ሌላ ፡
ረዳት ፡ የሌለኝ ፡ ብቸኛ ፡ የሆንሁ ፡ እኔን ፡ እር
ዳኝ ። የኃጢአተኞችን ፡ ክብራቸውን ፡ እንድ
ጠላ ፡ ያልተገረዙ ፡ የአሕዛብንም ፡ ምንጣፍ ፡
እንድጠላ ፡ የሰውን ፡ ልቡና ፡ አንተ ፡ መርም
ረህ ፡ ታውቃለህ ። በክብርሁበት ፡ ወራት ፡ የም ፵፪፤
ታይበት ፡ በራሴ ፡ ላይ ፡ ያለ ፡ የሚያስከብረኝ ፡
ጌጥ ፡ ደስ ፡ እንዳያሰኘኝ ፡ እንደ ፡ ደም ፡ ጨር
ቅም ፡ እንድጸየፈው ፡ በምከብርበትና ፡ በማር
ፍበትም ፡ ወራት ፡ እንዳላጌጠው ፡ መከራ
ዬን ፡ አንተ ፡ ታውቀዋለህ ። እኔ ፡ ባሪያህ ፡
የሐማን ፡ ማዕድ ፡ አልበላሁም ፡ የንጉሡም ፡ ፵፫፤
መጠጥ ፡ ደስ ፡ አያሰኘኝም ፡ ከወይናቸውም ፡
አልጠጣሁም ። አቤቱ ÷ ሁሉን ፡ የምትችል ፡ ፵፬፤
የአብርሃም ፡ ፈጣሪ ÷ በአንተ ፡ ደስ ፡ ይለ
ኛል ፡ እንጂ ፡ ከገባሁ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡
ድረስ ፡ እኔን ፡ ባሪያህን ፡ በእነርሱ ፡ ደስ ፡
አላለኝም ። ተስፋ ፡ የቈረጡ ፡ የእስራኤልን ፡ ፵፭፤
ልመና ፡ ስማ ÷ በኛ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ካደረጉ ፡ ከአ
ሕዛብም ፡ እጅ ፡ አድነን ÷ ከምፈራውም ፡ መከራ ፡
አድነኝ ።

ምዕራፍ ፡ ፭ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በሦስተኛው ፡ ቀን ፡ ልመና ፩፤
ዋን ፡ በጨረሰች ፡ ጊዜ ፡ የኀዘንዋን ፡ ልብስ ፡
አወለቀች ፡ የተድላ ፡ የደስታዋን ፡ ልብስ ፡ ለበ
ሰች ÷ የምታስፈራም ፡ ሆነች ፤ ሁሉን ፡ የሚመ
ለከት ፡ የሚያድን ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ለመነ
ችው ። ሁለቱን ፡ ደንገጥሮችዋን ፡ አስከትላ ፡
ሄደች ፡ ትወዳቃለችና ፡ ላንዲቱ ፡ ግን ፡ ትራራ
ላት ፡ ነበር ፤ ሁለተኛዪቱ ፡ ልብስዋን ፡ ተሸክማ ፡
ትከተላት ፡ ነበር ። እርስዋ ፡ ግን ፡ በጌጡ ፡ ሁሉ ፡
ፈጽማ ፡ አጊጣ ፡ አምሮባት ፡ ነበር ÷ ወደ ፡ ወዳ
ጆችዋ ፡ እንደምትሄድ ፡ ፊትዋም ፡ የሚያበራ ፡
ሆነ ÷ ልብዋ ፡ ግን ፡ ሞትን ፡ ከመፍራት ፡ የተ
ነሣ ፡ አዝኖ ፡ ነበር ። በሩን ፡ ሁሉ ፡ ገብታ ፡ ወደ ፡
ንጉሡ ፡ ደረሰች ፤ እርሱ ፡ ግን ፡ በጌትነቱ ፡ ዙፋን ፡
ላይ ፡ ተቀምጦ ፡ ነበር ።
ዋጋው ፡ ብዙ ፡ የሆነ ፡ ሁለንተናው ፡ዕንቍና ፡
ወርቅ ፡ ያለበት ፡ የሚያስፈራ ፡ ልብስን ፡ ለብሶ ፡
ነበር ÷ ፈጽሞም ፡ ያስፈራ ፡ ነበረ ። ፊቱም ፡
ከልቡናው ፡ ጋር ፡ ተለውጦ ፡ በዓይኑ ፡ መዓት ፡

አያት ፤ ንግሥቲቱ ፡ አስቴርም ፡ ከፍርሃት ፡ የተ
ነሣ ፡ እንደ ፡ ቅጠል ፡ ጠወለገች ፡ ለመውደቅም ፡
ተፍገመገመች ÷ በፊትዋ ፡ የምትሄድ ፡ የብላቴ
ናዋ ፡ ራስንም ፡ ተደገፈች ።
እግዚአብሔርም ፡ የንጉሡን ፡ ልቡና ፡ ወደ ፡
የዋህነት ፡ መለሰው ፡ ታግሣት ፡ ከዙፋኑ ፡ ተነ
ሥቶ ፡ ስቦ ፡ ከአጠገቡ ፡ አስቀመጣት ፡ በበጎ ፡
ቃልም ፡ ያበብላት ፡ ጀመር ፡— ያገራችን ፡ ሥር
ዓት ፡ ልዩ ፡ ነውና ፡ እንዳትሞች ፡ እኔ ፡ ወንድ
ምሽ ፡ ነኝ ፤ አስቴር ÷ ምን ፡ ሆንሽ ? አላት ።
፪፤ የወርቁን ፡ ዘንግ ፡ አንሥቶ ፡ በአንገትዋ ፡ ላይ ፡
አኖረው ÷ አቅፎ ፡ አድርጎ ፡ ይዞ ፡— ንገሪኝ ፡
አላት ። አንተ ፡ ድንቅ ፡ ነህና ÷ ፊትህም ፡ መፈ
ራትን ፡ የተመላ ፡ ነውና ፡ ከጌትነትህ ፡ መገለጥ ፡
የተነሣ ፡ ጌታዬ ፡ እንደ ፡ መልአከ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ሆነህ ፡ በየሁ ፡ ጊዜ ፡ ልቡናዬ ፡ ደነገጠ
ብኝ ። ስትናገርም ፡ ደንግጣ ፡ እንደ ፡ ቅጠል ፡
ጠወለገች ፡ በግምባርዋ ፡ ፍግም ፡ ብላ ፡ ወደ
ቀች ። ንጉሡ ፡ ደነገጠ ፡ ሠራዊቱም ፡ ሁሉ ፡
ደነገጡ ፡ ያበብሉዋትም ፡ ጀመር ።
፫፤ ንጉሡም ፡— ንግሥት ፡ አስቴር ፡ ሆይ ÷ የምት
ለምኚኝ ፡ ምንድር ፡ ነው ? የምትሺውስ ፡ ምን
ድር ፡ ነው ? እስከ ፡ መንግሥቴ ፡ እኩሌታ ፡
፬፤ እንኳ ፡ ቢሆን ፡ ይሰጥሻል ፡ አላት ። አስቴርም ፡—
ለንጉሡ ፡ መልካም ፡ ሆኖ ፡ ቢታይ ፡ ንጉሡ ፡
ወዳዘጋጀሁለት ፡ ግብገዣ ፡ ከሐማ ፡ ጋር ፡ ዛሬ ፡
፭፤ ይምጣ ፡ አለች ። ንጉሡም ፡— አስቴር ፡ እንዳ
ለች ፡ ይደረግ ፡ ዘንድ ፡ ሐማን ፡ አስቸኩሉት ፡
አለ ። ንጉሡና ፡ ሐማ ፡ አስቴር ፡ ወዳዘጋጀ
፮፤ ችው ፡ ግብገዣ ፡ መጡ ። ንጉሡም ፡ በወይኑ ፡
ጠጅ ፡ ግብዣ ፡ ሳለ ፡ አስቴርን ፡— የምትሺው ፡
ምንድር ፡ ነው ? ይሰጥሻል ፤ ልመናሽስ ፡ ምን
ድር ፡ ነው ? እስከ ፡ መንግሥቴ ፡ እኩሌታ ፡
፯፤ እንኳ ፡ ቢሆን ፡ ይደረግልሻል ፡ አላት ። አስቴ
ርም ፡ መልሳ ፡— ልመናዬና ፡ የምሻው ፡ ነገር ፡
፰፤ ይህ ፡ ነው ፤ በንጉሡ ፡ ዘንድ ፡ ሞገስ ፡ አግኝቼ ፡
እንደ ፡ ሆነ ÷ ልመናዬንም ፡ ይፈጽም ፡ ዘንድና ፡
የምሻውን ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ ንጉሡን ፡ ደስ ፡
ቢያሰኘው ÷ ንጉሡና ፡ ሐማ ፡ ወደማዘጋጅላ
ቸው ፡ ግብዣ ፡ ይምጡ ፤ እንደ ፡ ንጉሡም ፡
ነገር ፡ ነገ ፡ አደርጋለሁ ፡ አለች ።
፱፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ ሐማ ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ በል
ቡም ፡ ተደስቶ ፡ ወጣ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ መርዶክዮስ ፡
በንጉሡ ፡ በር ፡ ያለ ፡ መነሣትና ፡ ያለ ፡ መናወጥ ፡
ተቀምጦ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ ሐማ ፡ በመርዶክዮስ ፡
፲፤ ላይ ፡ እጅግ ፡ ተቈጣ ። ሐማ ፡ ግን ፡ ታግሦ ፡
ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሄደ ፤ ልከም ፡ ወዳጆቹንና ፡ ሚስ
፲፩፤ ቱን ፡ ዞሳራን ፡ አስጠራ ። ሐማም ፡ የሀብቱን ፡
ክብርና ፡ የልጆቹን ፡ ብዛት ÷ ንጉሡም ፡ ያከበረ
በትን ፡ ክብር ፡ ሁሉ ÷ በንጉሡም ፡ አዛውንትና ፡
ባሪያዎች ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ እንዳደረገው ፡
፲፪፤ አጫወታቸው ። ሐማም ፡— ንግሥቲቱ ፡ አስ
ቴር ፡ ወዳዘጋጀችው ፡ ግብዣ ፡ ከእኔ ፡ በቀር ፡
ከንጉሡ ፡ ጋር ፡ ማንንም ፡ አልጠራችም ፤ ደግሞ ፡
ነገ ፡ ከንጉሡ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ ተጠርቻ
ለሁ ። ነገር ፡ ግን ፡ አይሁዳዊው ፡ መርዶክዮስ ፡ ፲፫፤
በንጉሡ ፡ በር ፡ ተቀምጦ ፡ ከየሁ ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡
ለእኔ ፡ ምንምን ፡ አይጠቅምም ፡ አለ ። ሚስ ፲፬፤
ቱም ፡ ዞሳራና ፡ ወዳጆቹ ፡ ሁሉ ፡— ቁመቱ ፡
አምሳ ፡ ክንድ ፡ የሆነ ፡ ግንድ ፡ ይደረግ ÷ ነገም ፡
መርዶክዮስ ፡ ይሰቀልበት ፡ ዘንድ ፡ ለንጉሡ ፡
ተናገር ፤ ደስም ፡ ብሎህ ፡ ከንጉሡ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡
ግብዣው ፡ ግባ ፡ አሉት ። ነገራቸውም ፡ ሐማን ፡
ደስ ፡ አሰኘው ÷ ግንዱንም ፡ አስደረገ ።

ምዕራፍ ፡ ፮ ።

በዚያም ፡ ሌሊት ፡ እንቅልፍ ፡ ከንጉሡ ፡ ሸሸ ፤ ፩፤
የዘመኑንም ፡ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ ያመጡ ፡ ዘንድ ፡
አዘዘ ÷ በንጉሡም ፡ ፊት ፡ ተነበበ ። ደጁንም ፡ ፪፤
ከሚጠብቁት ፡ ከንጉሡ ፡ ጃንደረቦች ፡ ሁለቱ ፡
ገበታና ፡ ታራ ፡ እጃቸውን ፡ በንጉሡ ፡ በአርጤ
ክስስ ፡ ላይ ፡ ያነሡ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ፈለጉ ÷ መር
ዶክዮስ ፡ እንደ ፡ ነገረው ፡ ተጽፎ ፡ ተገኘ ። ንጉ ፫፤
ሡም ፡— ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ለመርዶክዮስ ፡ ምን ፡
ክብርና ፡ በጎነት ፡ ተደረገለት ? አለ ። ንጉሡ
ንም ፡ የሚያገለግሉ ፡ ብላቴኖች ፡— ምንም ፡
አልተደረገለትም ፡ አሉት ። ንጉሡም ፡— በአ ፬፤
ዳራሹ ፡ ማን ፡ አለ ? አለ ። ሐማም ፡ ባዘጋጀው ፡
ግንድ ፡ ላይ ፡ መርዶክዮስን ፡ ለማሰቀል ፡ ለን
ጉሡ ፡ ይናገር ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ቤት ፡
ወደ ፡ ውጭው ፡ አዳራሽ ፡ ገብቶ ፡ ነበር ። የንጉ ፭፤
ሡም ፡ ብላቴኖች ፡— እነሆ ፡ ሐማ ፡ በአዳራሹ ፡
ቆሞአል ፡ አሉት ። ንጉሡም ፡— ይግባ ፡ አለ ።
ሐማም ፡ ገባ ፤ ንጉሡም ፡— ንጉሡ ፡ ሊያከብ ፮፤
ረው ፡ ለሚወድደው ፡ ሰው ፡ ምን ፡ ይደረግለ
ታል ? አለው ። ሐማም ፡ በልቡ ፡— ንጉሡ ፡
ከእኔ ፡ ይልቅ ፡ ማንን ፡ ያከብር ፡ ዘንድ ፡ ይወድ
ዳል ? አለ ። ሐማም ፡ ንጉሡን ፡ እንዲህ ፡ ፯፤
አለው ፡— ንጉሡ ፡ ያከብረው ፡ ዘንድ ፡ ለሚወ
ድደው ፡ ሰው ፡ እንዲህ ፡ ይደረግ ፤ ንጉሡ ፡ የለ ፰፤
በሰው ፡ የክብር ፡ ልብስ ÷ ንጉሡም ፡ የተቀመጠ
በት ፡ ፈረስ ፡ ይምጣለት ÷ የንጉሡም ፡ ዘውድ ፡
በራሱ ፡ ላይ ፡ ይደረግ ፤ ልብሱንና ፡ ፈረሱንም ፡ ፱፤
ከንጉሡ ፡ አዛውንት ፡ በዋነኛው ፡ እጅ ፡ ያስረ
ክቡት ፤ ንጉሡም ፡ ያከብረው ፡ ዘንድ ፡ የሚወ
ድደውን ፡ ሰው ፡ ያልብሱት ፤ በፈረሱም ፡ ላይ ፡
አስቀምጠውት ፡ በከተማይቱ ፡ አደባባይ ፡ ያሳል
ፉት ፤ በፊቱም ፡— ንጉሡ ፡ ያከብረው ፡ ዘንድ ፡
ለሚወድደው ፡ ሰው ፡ እንዲህ ፡ ይደረግለታል ፡
ተብሎ ፡ አዋጅ ፡ ይነገር ።
ንጉሡም ፡ ሐማን ፡— ፍጠን ÷ እንደ ፡ ተናገ ፲፤
ርኸውም ፡ ልብሱንና ፡ ፈረሱን ፡ ውሰድ ፤ በንጉ
ሡም ፡ በር ፡ ለሚቀመጠው ፡ አይሁዳዊ ፡ ለመ
ርዶክዮስ ፡ እንዲሁ ፡ አድርግለት ፤ ከተናገርኸ
ውም ፡ ሁሉ ፡ ምንም ፡ አይቅር ፡ አለው ። ሐማም ፡ ፲፩፤
ልብሱንና ፡ ፈረሱን ፡ ወሰደ ÷ መርዶክዮስንም ፡
አለበሰው ÷ በፈረሱም ፡ ላይ ፡ አስቀመጠው ÷
በከተማይቱም ፡ አደባባይ ፡ በፊቱ ፡ አሳለፈው ።

በፊቱም ፡— ንጉሡ ፡ ያከብረው ፡ ዘንድ ፡ ለሚ
ወድደው ፡ ሰው ፡ እንዲህ ፡ ይደረግለታል ፡ ብሎ ፡
፲፪ አዋጅ ፡ ነገረ ። መርዶክዮስም ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡
በር ፡ ተመለሰ ። ሐማ ፡ ግን ፡ አዝኖና ፡ ራሱን ፡
፲፫ ተከናንቦ ፡ ቸኵሎ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሄደ ። ሐማም ፡
ለሚስቱ ፡ ለዞሳራና ፡ ለወዳጆቹ ፡ ሁሉ ፡ ያገኘ
ውን ፡ ሁሉ ፡ አጫወታቸው ። ጥበበኞቹና ፡
ሚስቱ ፡ ዞሳራም ፡— በፊቱ ፡ መውደቅ ፡ የጀ
መርህለት ፡ መርዶክዮስ ፡ ከአይሁድ ፡ ወገን ፡
የሆነ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በፊቱ ፡ ፈጽሞ ፡ ትወድቃ
፲፬ ለህ ፡ እንጂ ፡ አታሸንፈውም ፡ አሉት ። እነር
ሱም ፡ ሲናገሩት ፡ ሳሉ ፡ እነሆ ፡ የንጉሡ ፡ ጃን
ደረቦች ፡ መጡ ፤ አስቴርም ፡ ወዳዘጋጀችው ፡
ግብዣ ፡ ይመጣ ፡ ዘንድ ፡ ሐማን ፡ አስቸኰሉት ።

ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ ንጉሡና ፡ ሐማም ፡ ከንግሥቲቱ ፡ ከአስቴር ፡
፪ ጋር ፡ ለመጠጣት ፡ መጡ ። በሁለተኛውም ፡
ቀን ፡ ንጉሡ ፡ በወይኑ ፡ ጠጅ ፡ ግብዣ ፡ ሳለ ፡ አስ
ቴርን ፡— ንግሥት ፡ አስቴር ፡ ሆይ ፤ የምትለም
ኚኝ ፡ ምንድር ፡ ነው ? ይሰጥሻል ፤ የምትሺ
ውስ ፡ ምንድር ፡ ነው ? እስከ ፡ መንግሥቴ ፡
እኵሌታ ፡ እንኳ ፡ ቢሆን ፡ ይደረግልሻል ፡ አላት ።
፫ ንግሥቲቱም ፡ አስቴር ፡ መልሳ ፡— ንጉሥ ፡
ሆይ ፤ በአንተ ፡ ዘንድ ፡ ሞገስ ፡ አግኝቼ ፡
እንደ ፡ ሆነ ፤ ንጉሡንም ፡ ደስ ፡ ቢያሰኘው ፤
ሕይወቴ ፡ በልመናዬ ፡ ሕዝቤም ፡ በመሻቴ ፡
፬ ይሰጠኝ ፤ እኔና ፡ ሕዝቤ ፡ ለመጥፋትና ፡
ለመገደል ፡ ለመደምሰስም ፡ ተሸጠናልና ።
ባሪያዎች ፡ ልንሆን ፡ ተሸጠን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
ዝም ፡ ባልሁ ፡ ነበር ፤ የሆነ ፡ ሆኖ ፡ ጠላቱ ፡
የንጉሡን ፡ ጉዳት ፡ ለማቅናት ፡ ባልቻለም ፡
፭ ነበር ፡ አለች ። ንጉሡም ፡ አርጤክስስ ፡ ንግሥ
ቲቱን ፡ አስቴርን ፡— ይህን ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡
በልቡ ፡ የደፈረ ፡ ማን ፡ ነው ? እርሱስ ፡ ወዴት ፡
፮ ነው ? ብሎ ፡ ተናገራት ። አስቴርም ፡— ያ ፡ ጠላ
ትና ፡ ባለጋራ ፡ ሰው ፡ ክፉው ፡ ሐማ ፡ ነው ፡
አለች ። ሐማም ፡ በንጉሡና ፡ በንግሥቲቱ ፡
፯ ፊት ፡ ደነገጠ ። ንጉሡም ፡ ተቈጥቶ ፡ የወይን ፡
ጠጅ ፡ ከመጠጣቱ ፡ ተነሣ ፤ ወደ ፡ ንጉሡም ፡
ቤት ፡ አታክልት ፡ ውስጥ ፡ ሄደ ። ሐማም ፡ ከን
ጉሡ ፡ ዘንድ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ እንደ ፡ ታሰበበት ፡
አይቶአልና ፡ ከንግሥቲቱ ፡ ከአስቴር ፡ ሕይወ
፰ ቱን ፡ ይለምን ፡ ዘንድ ፡ ቆመ ። ንጉሡም ፡
ከቤቱ ፡ አታክልት ፡ ወደ ፡ ወይን ፡ ጠጁ ፡ ግብዣ ፡
ስፍራ ፡ ተመለሰ ፤ ሐማም ፡ አስቴር ፡ ባለችበት ፡
አልጋ ፡ ላይ ፡ ወድቆ ፡ ነበር ። ንጉሡም ፡—
ደግሞ ፡ በቤቴ ፡ በእኔ ፡ ፊት ፡ ንግሥቲቱን ፡ ይጋ
ፉታልን ? አለ ። ይህም ፡ ቃል ፡ ከንጉሡ ፡ አፍ ፡
፱ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ የሐማን ፡ ፊት ፡ ሸፈኑት ። በንጉ
ሡም ፡ ፊት ፡ ካሉት ፡ ጃንደረቦች ፡ አንዱ ፡
ሐርቦና ፡— እነሆ ፡ ሐማ ፡ ለንጉሡ ፡ በጎ ፡ ለተ
ናገረው ፡ ለመርዶክዮስ ፡ ያሠራው ፡ ርዝመቱ ፡
አምሳ ፡ ክንድ ፡ የሆነው ፡ ግንድ ፡ በሐማ ፡ ቤት ፡
ተተክሎአል ፡ አለ ። ንጉሡም ፡— በእርሱ ፡
፲ ላይ ፡ ስቀሉት ፡ አለ ። ሐማንም ፡ ለመርዶክ
ዮስ ፡ ባዘጋጀው ፡ ግንድ ፡ ላይ ፡ ሰቀሉት ፤ በዚ
ያም ፡ ጊዜ ፡ የንጉሡ ፡ ቍጣ ፡ በረደ ።

ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ በዚያም ፡ ቀን ፡ ንጉሡ ፡ አርጤክስስ ፡ የአይ
ሁድን ፡ ጠላት ፡ የሐማን ፡ ቤት ፡ ለንግሥቲቱ ፡
ለአስቴር ፡ ሰጠ ። አስቴርም ፡ ለእርስዋ ፡ ምን ፡
እንደ ፡ ሆነ ፡ ነግራው ፡ ነበርና ፡ መርዶክዮስ ፡
፪ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ፊት ፡ ገባ ። ንጉሡም ፡ ከሐማ ፡
ያወለቀውን ፡ ቀለበቱን ፡ አወጣ ፤ ለመርዶክዮ
ስም ፡ ሰጠው ። አስቴርም ፡ በሐማ ፡ ቤት ፡ ላይ ፡
መርዶክዮስን ፡ ሾመች ።
፫ አስቴርም ፡ እንደ ፡ ገና ፡ በንጉሡ ፡ ፊት ፡ ተና
ገረች ፤ በእግሩም ፡ ላይ ፡ ወድቃ ፡ እያለቀሰች ፡
የአጋጋዊውን ፡ የሐማን ፡ ክፋትና ፡ በአይሁድ ፡
ላይ ፡ የተተነኰለውን ፡ ተንኰል ፡ ይሽር ፡ ዘንድ ፡
፬ ለመነችው ። ንጉሡም ፡ የወርቁን ፡ ዘንግ ፡ ለአ
ስቴር ፡ ዘረጋላት ፤ አስቴርም ፡ ተነሥታ ፡ በን
፭ ጉሡ ፡ ፊት ፡ ቆመችና ፡— ንጉሡን ፡ ደስ ፡ ቢያ
ሰኘው ፤ በፊቱም ፡ ሞገስ ፡ አግኝቼ ፡ እንደ ፡
ሆነ ፤ ይህም ፡ ነገር ፡ በፊቱ ፡ ቅን ፡ ቢሆን ፤ እኔም ፡
በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ተወድጄ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፤ አጋ
ጋዊው ፡ የሐመዳቱ ፡ ልጅ ፡ ሐማ ፡ በንጉሡ ፡
አገር ፡ ሁሉ ፡ ያሉትን ፡ አይሁድ ፡ ለማጥፋት ፡
የጻፈው ፡ ተንኰል ፡ ይገለበጥ ፡ ዘንድ ፡ ይጻፍ ።
፮ እኔ ፡ በሕዝቤ ፡ ላይ ፡ የሚወርደውን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡
አይ ፡ ዘንድ ፡ እንዴት ፡ እችላለሁ ? ወይስ ፡ የዘ
መዶቼን ፡ ጥፋት ፡ አይ ፡ ዘንድ ፡ እንዴት ፡ እች
፯ ላለሁ ? አለች ። ንጉሡም ፡ አርጤክስስ ፡ ንግ
ሥቲቱን ፡ አስቴርንና ፡ አይሁዳዊውን ፡ መርዶ
ክዮስን ፡— እነሆ ፡ የሐማን ፡ ቤት ፡ ለአስቴር ፡
ሰጥቻለሁ ፤ እርሱም ፡ እጆቹን ፡ በአይሁድ ፡
ላይ ፡ ስለ ፡ ዘረጋ ፡ በግንድ ፡ ላይ ፡ ተሰቀለ ።
፰ በንጉሡ ፡ ስም ፡ የተጻፈና ፡ በንጉሡ ፡ ቀለበት ፡
የታተመ ፡ አይገለበጥምና ፡ እናንተ ፡ ደግሞ ፡
ደስ ፡ የሚያሰኛችሁን ፡ በንጉሡ ፡ ስም ፡ ስለ ፡
አይሁድ ፡ ጻፉ ፤ በንጉሡም ፡ ቀለበት ፡ አትሙ ፡
አላቸው ።
፱ በዚያን ፡ ጊዜም ፡ ኒሳን ፡ በተባለው ፡ በመጀ
መሪያው ፡ ወር ፡ ከወሩም ፡ በሀያ ፡ ሦስተኛው ፡
ቀን ፡ የንጉሡ ፡ ጸሐፊዎች ፡ ተጠሩ ፤ መርዶክ
ዮስም ፡ ስለ ፡ አይሁድ ፡ እንዳዘዘው ፡ ሁሉ ፡
ከህንድ ፡ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ድረስ ፡
በመቶ ፡ ሀያ ፡ ሰባቱ ፡ አገሮች ፡ ላሉ ፡ ሹማም
ትና ፡ አለቆች ፡ አዛውንትም ፡ ለእያንዳንዱም ፡
አገር ፡ እንደ ፡ ጽሕፈቱ ፡ ለእያንዳንዱም ፡ ሕዝብ ፡
እንደ ፡ ቋንቋው ፡ ለአይሁድም ፡ እንደ ፡ ጽሕፈ
፲ ታቸውና ፡ እንደ ፡ ቋንቋቸው ፡ ተጻፈ ። በንጉ
ሡም ፡ በአርጤክስስ ፡ ስም ፡ አስጻፈው ፤ በን
ጉሡም ፡ ቀለበት ፡ አሳተመው ፤ ደብዳቤውንም ፡
በንጉሡ ፡ ፈረስ ፡ ቤት ፡ በተወለዱት ፤ ለንጉ
ሡም ፡ አገልግሎት ፡ በተለዩ ፡ በፈጣን ፡ ፈረ

ሶች፡ በተቀመጡ፡ መልእክተኞች፡ እጅ፡ ሰደ
፲፩፤ ደው። በዚያም፡ ደብዳቤ፡ በከተሞቹ፡ ሁሉ፡
የሚኖሩት፡ አይሁድ፡ እንዲሰበሰቡ ÷ ለሕይወ
ታቸውም፡ እንዲቆሙ ÷ በጥል፡ የሚነሡባቸ
ውን፡ የሕዝቡንና፡ የአገሩን፡ ሠራዊት፡ ሁሉ፡
ከሕፃናቶቻቸውና፡ ከሴቶቻቸው፡ ጋር፡ እንዲ
ያጠፉና፡ እንዲገድሉ፡ እንዲደመስሱም ÷ ምር
ኮአቸውንም፡ እንዲዘርፉ፡ ንጉሡ፡ ፈቀደላ
፲፪፤ ቸው። ይህም፡ አዳር፡ በሚባለው፡ በአሥራ፡
ሁለተኛው፡ ወር፡ በአሥራ፡ ሦስተኛው፡ ቀን፡
በንጉሡ፡ በአርጤክስስ፡ አገሮች፡ ሁሉ፡ በአ
ንድ፡ ቀን፡ እንዲሆን፡ ነው።
(፩) የተጻፉ፡ የገናናው፡ ንጉሥ፡ የአርጤክስስ፡
እነዚያ፡ መጻሕፍቶች፡ ለኢትዮጵያና፡ ለህንድ፡
አገር፡ ለመቶ፡ ሀያ፡ ሰባቱም፡ አገሮች፡ ለመኳ
ንንቱና፡ ለሹማምቱም፡ ይድረሱ፡ ተድላ፡
ደስታን፡ በማብዛት፡ በመራራትም፡ ለምትረቡ
አቸው፡ ለምትጠቅሙአቸው፡ ለእናንተ፡ በኛ፡
(፪) መልክት። ብዙ፡ ሰዎች፡ ተድላ፡ ደስታን፡
ያድርጉላችሁ ÷ ነገር፡ ግን፡ ፈጥነው፡ ስለ፡
(፫) ተሾሙ፡ እንኳ፡ ትዕቢትን፡ አበዙ። የሚረቡ
አቸውን፡ ሰዎች፡ ይተነኰሉባቸው፡ ዘንድ፡
ያስባሉ፡ እንጂ፡ ጥጋባቸውን፡ መታገሥ፡ የማ
ይችሉ፡ እንኳ፡ በእነርሱ፡ ክፉ፡ ነገር፡ ያደርጉ፡
ዘንድ፡ የሚወድዱ፡ በሚገዙልን፡ በእስራኤል፡
(፬) ብቻ፡ አይደለም። ዳግመኛም፡ አዲስ፡ በለወ
ጎች፡ እንደ፡ መሆናቸው፡ በመታበይ፡ ራሳቸ
ውን፡ ያገናሉ፡ ያከብራሉ፤ ሁልጊዜ፡ ሁሉን፡
የሚመለከት፡ የእግዚአብሔርንም፡ ምስጋና፡
ያጠፋሉ፡ እንጂ፡ የሰውን፡ ምስጋና፡ ብቻ፡
የሚያጠፉ፡ አይደሉም። ኃጢአትን፡ ከሚጠላ፡
ከእግዚአብሔር፡ ፍርድ፡ የሚያመልጡ፡ ይመ
(፭) ስላቸዋል። ነገር፡ ግን፡ የሚገዙልን፡ በመስማ
ማት፡ ይገዙልን፡ ያገለግሉን፡ ዘንድ፡ የታመና
ቸው፡ የተዘጋጁ፡ የብዙ፡ ሰዎች፡ ንጹሕ፡
ደምን፡ በማፍሰስ፡ እነዚያ፡ እንኳ፡ አንድ፡
(፮) ሆኑ፡ ክፉ፡ ነገርን፡ በማሰብ። ሐሰትንም፡ በም
ክር፡ በጽጥታና፡ በየውሃት፡ የምትኖር፡ መንግ
ሥትን፡ አታለው፡ የሚያስጨንቅ፡ መከራን፡
(፯) መከሩባቸው። ነገር፡ ግን፡ በጎ፡ ነገርን፡ በማ
ሰብ፡ ይቀራል፡ ይኸውም፡ ከኛ፡ አስቀድሞ፡
ከነበሩ፡ ሰዎች፡ ይልቅ፡ የምንበልጥ፡ አይደ
ለም፡ ሥርዓቱን፡ እንደ፡ ተቀበልነው፡ እንደ
(፰) ዚሁ፡ ጸንተን፡ ኖርን፡ እንጂ። በሚገባ፡ መፍ
ረድ፡ የማይችሉ፡ እንኳ፡ የማይገባቸውን፡
ጌትነት፡ አግኝተዋልና፡ ነገር፡ ግን፡ ከዚህ፡
በኋላ፡ ያለ፡ ሥራት፡ የተደረገውን፡ ነገር፡ እን
(፱) መረምራለን፤ ከዚህም፡ በኋላ፡ ያለ፡ ሁከት፡
መንግሥታችን፡ ጸንታ፡ የምትኖርበትን፡ ነገር፡
አሰብን፤ የተገለጠውንም፡ ፍርድ፡ በየዋህነት፡
(፲) እንፈርዳለን። የመቄዶን፡ ወገን፡ የሆነ፡ የሐ
መዳቱ፡ ልጅ፡ ሐማ፡ ግን፡ ከእውነት፡ ነገር፡
የወጣ፡ እንደ፡ መሆኑ ÷ ከፋርስ፡ ሥርዓትም፡
የወጣ፡ እንደ፡ መሆኑ፡ ለኛ፡ ቸርነት፡ ከማድረግ፡
እጅግ፡ የራቀ፡ ሆነ። እርሱም፡ በሕዝቡ፡ ላይ፡ (፲፩)
ሁሉ፡ በለሚልነትንና፡ ሹመትን፡ አግኝቶ፡ ከኛ፡
ጋር፡ ሲኖር፡ የተለየ፡ ሆነ፤ ይልቁንም፡ አባታ
ችን፡ እስከንለው፡ ድረስ፡ የመንግሥታችንም፡
ሁለተኛ፡ እስከንለው፡ ከዙፋናችንም፡ ጋር፡
በለሚልነትን፡ አግኝቶ፡ ይልቁንም፡ ሹመትን፡
አግኝቶ። ኩራትን፡ አበዛ፡ እንጂ፡ ዳግመኛ፡ (፲፪)
ይህ፡ አልበቃውም፤ ከመንግሥታችን፡ ያጠ
ጣን፡ ዘንድ፡ ሰውነታችንንም፡ ወደ፡ ጥፋት፡
ይወስድ፡ ዘንድ፡ አሰበ። በሁሉ፡ የሚጠቅ (፲፫)
መን፡ የሚያድነንን፡ የሚያገለግለንን፡ መርዶክ
ዮስን፡ ግን፡ ያለ፡ ነቀፋ፡ የመንግሥታችን፡
ተባባሪ፡ የምትሆን፡ አስቴርንም፡ ነገርን፡ በማ
ጣፈጥና፡ በብዙ፡ መተንኰል፡ ከወገኖቻቸው፡
ሁሉ፡ ጋር፡ ያጠፋቸው፡ ዘንድ፡ አልቻለም። በየዋ (፲፬)
ህነት፡ እንኖራለንና፡ ስለዚህ፡ ነገር፡ የፋርስን፡
መንግሥት፡ አገኘን ÷ እሱ፡ ግን፡ በመቄዶና
ውያን፡ ሥርዓት፡ ያጠፋን፡ ዘንድ፡ ወደደ።
የሐጋቸው፡ አንዋወር፡ በእውነት፡ ነው፡ (፲፭)
እንጂ፡ እኛ፡ ግን፡ ያጠፋቸው፡ ዘንድ፡ የወደደ፡
እስራኤልን፡ በኃጢአት፡ እንዳይደሉ፡ አገኘ
ናቸው። በእውነት፡ ከፍ፡ ያለ፡ ገናና፡ የሆነ፡ (፲፮)
የእግዚአብሔር፡ ልጆች፡ ናቸው፤ ከእኛ፡ አስ
ቀድሞ፡ ለነበሩ፡ ለአባቶቻችንና፡ ለእኛ፡ መን
ግሥትን፡ ያዘጋጀ፡ እኛንም፡ እንደ፡ ልቡናችን፡
ቅንነት፡ ከመከራ፡ ያዳነን፡ እግዚአብሔር፡ ሕያው፡
ነው። ነገር፡ ግን፡ ትውልዱ፡ የአጋግ፡ ወገን፡ የሆነ፡ (፲፯)
የሐማን፡ ትእዛዝ፡ የላከውንም፡ የመጽሐፉን፡
ቃል፡ ባትሰሙ፡ በጎ፡ ነገር፡ ታደርጋላችሁ።
እርሱ፡ ይህንን፡ ነገር፡ አስቦበታልና፡ ሁሉን፡ (፲፰)
የሚገዛ፡ እግዚአብሔር፡ ፈጥኖ፡ ፍዳውን፡ ስለ፡
ከፈለው፡ ከወገኖቹ፡ ሁሉ፡ ጋር፡ በሱሳ፡ አገር፡
አደባባይ፡ ተሰቀለ። ይህችን፡ መጽሐፍ፡ ዘር (፲፱)
ግታችሁ፡ ገልጣችሁ፡ በቦታው፡ ሁሉ፡ አሳዩ
አት፡ እስራኤልንም፡ በሥርዓታቸው፡ ጸንተው፡
ይኖሩ፡ ዘንድ፡ ተዉአቸው። አሥራ፡ ሁለተ (፳)
ኛው፡ ወር፡ የሚሆን፡ አዳር፡ በባተ፡ በአሥራ፡
ሦስተኛው፡ ቀን፡ ከዚያች፡ ቀን፡ ጀምሮ፡ እስ
ከዚች፡ ሰዓት፡ ድረስ፡ ቀድሞ፡ ባስጨነቋቸው፡
በመከራቸው፡ ወራት፡ እርዱአቸው። ከሁሉ፡ (፳፩)
የሚጸና፡ እግዚአብሔርም፡ ስለ፡ ጥፋታቸው፡
ፋንታ፡ ለተመረጡ፡ ወገኖች፡ ለእስራኤል፡
ተድላ፡ ደስታ፡ አደረገላቸው። እናንተም፡ (፳፪)
ስማችሁ፡ እንደ፡ ተጠራ፡ በበዓላችሁ፡ በተለ
የም፡ ቀን፡ እንደዚሁ፡ ተድላ፡ ደስታ፡ አድርጉ።
አሁንም፡ ከዚህ፡ በኋላ፡ ለፋርስ፡ ሰዎች፡ በጎ፡ (፳፫)
ነገር፡ ለሚያደርጉ፡ ለእስራኤል፡ ደኅንነትን፡
ይሆናል። እኛንም፡ ይወነጅሉ፡ ዘንድ፡ ለሚ
ወድዱ፡ ሰዎች፡ የጥፋታቸው፡ መታሰቢያ፡
ይሆናል። አገሩ፡ ሁሉ፡ በአራቱ፡ ማዕዘን፡ (፳፬)
እንዲህ፡ ያላደረገ፡ መንደሩም፡ ከተማው፡ ሁሉ፡
በእሳትና፡ በጦር፡ በመዓት፡ ይጠፋል፤ በወፎ
ችና፡ በአውሬዎችም፡ ፈጽሞ፡ ጥፋት፡ ይደረ
ጋል፡ እንጂ፡ ጥፋት፡ የሚደረግ፡ በሰው፡ ብቻ፡

፲፫፤ አይደለም ። አይሁድም ፡ ጠላቶቻቸውን ፡ እን
ዲበቀሉ ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ ይዘጋጁ ፡ ዘንድ ፡ የደብ
ዳቤው ፡ ቅጅ ፡ በየአገሩ ፡ ላሉ ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡
፲፬፤ ታወጀ ። ለንጉሡ ፡ አገልግሎት ፡ በተለዩ ፡
በፈጣን ፡ ፈረሶች ፡ የተቀመጡት ፡ መልእክተ
ኞች ፡ በንጉሡ ፡ ትእዛዝ ፡ ተርበትብተውና ፡
ቸኵለው ፡ ወጡ ፤ አዋጁም ፡ በሱሳ ፡ ግንብ ፡
ተነገረ ።
፲፭፤ መርዶክዮስም ፡ በሰማያዊና ፡ በነጭ ፡ ሐር ፡
የተሠራውን ፡ የንጉሡን ፡ የክብር ፡ ልብስ ፡
ለብሶ ፡ ታላቅም ፡ የወርቅ ፡ አክሊል ፡ ደፍቶ ፡
ከጥሩ ፡ በፍታና ፡ ከሐምራዊ ፡ ግምጃ ፡ የተሠራ ፡
መጐናጸፊያ ፡ ተጐናጽፎ ፡ ከንጉሡ ፡ ፊት ፡
ወጣ ፤ የሱሳም ፡ ከተማ ፡ ደስ ፡ አላት ፥ እልልም ፡
፲፮፤ አለች ። ለአይሁድም ፡ ብርሃንና ፡ ደስታ ፡ ተድ
፲፯፤ ላና ፡ ክብርም ፡ ሆነ ። የንጉሡም ፡ ትእዛዝና ፡
አዋጅ ፡ በደረሰበት ፡ አገርና ፡ ከተማ ፡ ሁሉ ፡
ለአይሁድ ፡ ደስታና ፡ ተድላ ፥ የግብዣም ፡ ቀን ፡
መልካምም ፡ ቀን ፡ ሆነ ። አይሁድንም ፡ መፍ
ራት ፡ ስለ ፡ ወደቀባቸው ፡ ከምድር ፡ አሕዛብ ፡
ብዙ ፡ ሰዎች ፡ አይሁድ ፡ ሆኑ ።

ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩፤ አዳር ፡ በሚባለውም ፡ በአሥራ ፡ ሁለተኛው ፡
ወር ፡ ከወሩም ፡ በአሥራ ፡ ሦስተኛው ፡ ቀን ፥
የንጉሡ ፡ ትእዛዝና ፡ አዋጅ ፡ ሊፈጸምበት ፡ በነ
በረው ፡ ቀን ፥ የአይሁድ ፡ ጠላቶች ፡ ሊሠለጥ
ኑባቸው ፡ በነበረው ፡ ቀን ፥ አይሁድ ፡ በጠላቶ
ቻቸው ፡ ላይ ፡ እንዲሠለጥኑ ፡ ነገሩ ፡ ተገለበጠ ።
፪፤ አይሁድም ፡ ክፉታቸውን ፡ በሚሹት ፡ ሰዎች ፡
ላይ ፡ እጃቸውን ፡ ይዘረጉ ፡ ዘንድ ፡ በንጉሡ ፡
በአርጤክስስ ፡ አገሮች ፡ ሁሉ ፡ በነበሩ ፡ ከተሞ
ቻቸው ፡ ውስጥ ፡ ተሰበሰቡ ፤ እነርሱንም ፡ መፍ
ራት ፡ በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ወድቆ ፡ ነበርና ፡
እነርሱን ፡ የሚቃወም ፡ ሰው ፡ አልነበረም ።
፫፤ መርዶክዮስን ፡ መፍራት ፡ በላያቸው ፡ ስለ ፡
ወደቀ ፡ በየአገሩ ፡ የነበሩ ፡ አዛውንትና ፡ ሹማ
ምቶች ፡ አለቆችም ፥ የንጉሡንም ፡ ሥራ ፡ የሚ
፬፤ ሠሩቱ ፡ ሁሉ ፡ አይሁድን ፡ አገዙ ። ያ ፡ ሰው ፡
መርዶክዮስ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ እያለ ፡ ስለ ፡ ሄደ ፡
በንጉሡ ፡ ቤት ፡ ታላቅ ፡ ሆኖ ፡ ነበርና ፥ የመር
ዶክዮስም ፡ ዝና ፡ በየአገሩ ፡ ሁሉ ፡ ተሰምቶ ፡
፭፤ ነበርና ። አይሁድም ፡ ጠላቶቻቸውን ፡ ሁሉ ፡
በሰይፍ ፡ እየመቱ ፡ ገደሉአቸው ፥ አጠፉአቸ
ውም ፤ በሚጠሉአቸውም ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ወደዱ ፡
፮፤ አደረጉባቸው ። አይሁድም ፡ በሱሳ ፡ ግንብ ፡
አምስት ፡ መቶ ፡ ያህል ፡ ሰዎች ፡ ገደሉ ፡ አጠ
፯፤፰፤ ፉም ። ፈርሰኔስ ፥ ደልፎን ፥ ፋስጋ ፥ ፋረዳታ ፥
፱፤ በርያ ፥ ሰርበክ ፥ መርመሲማ ፥ ሩፋዮስ ፥ አርሳ
፲፤ ዮስ ፥ ዛቡታዮስ ፡ የሚባሉትን ፥ የሐመዳቱን ፡
ልጅ ፡ የአይሁድን ፡ ጠላት ፡ አሥሩን ፡ የሐማን ፡
ልጆች ፡ ገደሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ብዝበዛው ፡
እጃቸውን ፡ አልዘረጉም ።
፲፩፤ በዚያም ፡ ቀን ፡ በሱሳ ፡ ግንብ ፡ የተገደሉት ፡
ሰዎች ፡ ቍጥር ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ መጣ ። ንጉ ፲፪፤
ሡም ፡ ንግሥቲቱን ፡ አስቴርን ፡— አይሁድ ፡
በሱሳ ፡ ግንብ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ሰዎችንና ፡
አሥሩን ፡ የሐማ ፡ ልጆች ፡ ገደሉ ፡ አጠፉአቸ
ውም ፤ በቀሩትስ ፡ በንጉሡ ፡ አገሮች ፡ እንዴት ፡
አድርገው ፡ ይሆን ! አሁንስ ፡ ልመናሽ ፡ ምን
ድር ፡ ነው ? ይሰጥሻል ፤ ሌላስ ፡ የምትሺው ፡
ምንድር ፡ ነው ? ይደረጋል ፡ አላት ። አስቴ ፲፫፤
ርም ፡— ንጉሡን ፡ ደስ ፡ ቢያሰኘው ፡ በሱሳ ፡
የሚኖሩ ፡ አይሁድ ፡ ዛሬ ፡ እንደ ፡ ተደረገው ፡
ትእዛዝ ፡ ነገ ፡ ደግሞ ፡ ያድርጉ ፤ አሥሩም ፡
የሐማ ፡ ልጆች ፡ በግንድ ፡ ላይ ፡ ይሰቀሉ ፡ አለች ።
ንጉሡም ፡ ይህ ፡ ይደረግ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፤ አዋ ፲፬፤
ጅም ፡ በሱሳ ፡ ተነገረ ፤ አሥሩንም ፡ የሐማን ፡
ልጆች ፡ ሰቀሉ ። በሱሳም ፡ የነበሩ ፡ አይሁድ ፡ ፲፭፤
አዳር ፡ በሚባለው ፡ ወር ፡ በአሥራ ፡ አራተ
ኛው ፡ ቀን ፡ ደግሞ ፡ ተሰብስበው ፡ በሱሳ ፡
ሦስት ፡ መቶ ፡ ያህል ፡ ሰዎች ፡ ገደሉ ፤ ነገር ፡
ግን ፡ ወደ ፡ ብዝበዛው ፡ እጃቸውን ፡ አልዘረ
ጉም ።
የቀሩትም ፡ በንጉሡ ፡ አገር ፡ ያሉ ፡ አይሁድ ፡ ፲፮፤
ተሰብስበው ፡ ለሕይወታቸው ፡ ቆሙ ፥ ከጠላቶ
ቻቸውም ፡ ዐረፉ ፤ ከሚጠሉአቸውም ፡ ሰባ ፡
አምስት ፡ ሺህ ፡ ገደሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ብዝበ
ዛው ፡ እጃቸውን ፡ አልዘረጉም ። አዳር ፡ በሚ ፲፯፤
ባለው ፡ ወር ፡ በአሥራ ፡ ሦስተኛው ፡ ቀን ፡ ይህ ፡
ተደረገ ፤ በአሥራ ፡ አራተኛውም ፡ ቀን ፡ ዐረፉ ፥
የግብዣና ፡ የደስታም ፡ ቀን ፡ አደረጉ ። በሱሳ ፡ ፲፰፤
የነበሩት ፡ አይሁድ ፡ ግን ፡ በአሥራ ፡ ሦስተኛ
ውና ፡ በአሥራ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ ተሰበሰቡ ፤
በአሥራ ፡ አምስተኛውም ፡ ቀን ፡ ዐረፉ ፥ የመ
ጠጥና ፡ የደስታም ፡ ቀን ፡ አደረጉት ። ስለዚ ፲፱፤
ህም ፡ በመንደሮችና ፡ በልተመሸጉ ፡ ከተሞች ፡
የሚኖሩ ፡ አይሁድ ፡ አዳር ፡ በሚባለው ፡ ወር ፡
አሥራ ፡ አራተኛውን ፡ ቀን ፡ የደስታና ፡ የመ
ጠጥ ፡ የመልካምም ፡ ቀን ፥ እርስ ፡ በርሳቸ
ውም ፡ስጦታ ፡ የሚሰጣጡበት ፡ ቀን ፡ ያደርጉ
ታል ።
መርዶክዮስም ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ጻፈ ፥ በንጉ ፳፤
ሡም ፡ በአርጤክስስ ፡ አገሮች ፡ ሁሉ ፡ በቅርብና ፡
በሩቅ ፡ ወዳሉት ፡ አይሁድ ፡ ሁሉ ፡ ደብዳቤዎ
ችን ፡ ላከ ። በየዓመቱም ፡ አዳር ፡ በሚባለው ፡ ፳፩፤
ወር ፡ አሥራ ፡ አራተኛውና ፡ አሥራ ፡ አምስተ
ኛው ፡ ቀን ፥ አይሁድ ፡ ከጠላቶቻቸው ፡ ዕረ ፳፪፤
ፍትን ፡ ያገኙበት ፡ ቀን ፥ ወሩም ፡ ከኀዘን ፡
ወደ ፡ ደስታ ፡ ከልቅሶም ፡ ወደ ፡ መልካም ፡
ቀን ፡ የተለወጠበት ፡ ወር ፡ ሆኖ ፡ ይጠብቁት ፡
ዘንድ ፥ የግብዣና ፡ የደስታም ፡ ቀን ፥ እርስ ፡
በርሳቸውም ፡ ስጦታ ፡ የሚሰጣጡበትና ፡ ለድ
ሆች ፡ ስጦታ ፡ የሚሰጡበት ፡ ቀን ፡ ያደርጉት ፡
ዘንድ ፡ አዘዛቸው ። አይሁድም ፡ ለመሥራት ፡ ፳፫፤
የጀመሩትን ፥ መርዶክዮስም ፡ የጻፈላቸውን ፡
ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ተቀበሉት ፤ አጋጋዊው ፡ የሐ ፳፬፤
መዳቱ ፡ ልጅ ፡ የአይሁድ ፡ ሁሉ ፡ ጠላት ፡ ሐማ ፡

አይሁድን ፡ ያጠፋ ፡ ዘንድ ፡ ተተንኰሎ ፡ ነበር ፤
ሊደመስሳቸውና ፡ ሊያጠፋቸውም ፡ ፋር ፡ የሚ
፳፭፤ ባል ፡ ዕጣ ፡ ጥሎ ፡ ነበር ። አስቴርም ፡ ወደ ፡
ንጉሡ ፡ ፊት ፡ በገባች ፡ ጊዜ ፡ በአይሁድ ፡ ላይ ፡
የተተነኰለው ፡ ክፉ ፡ ተንኰል ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡
እንዲመለስ ÷ እርሱና ፡ ልጆቹም ፡ በግንድ ፡
ላይ ፡ እንዲሰቀሉ ፡ በደብዳቤው ፡ አዘዘ ።
፳፮፤ ስለዚህም ፡ እነዚህ ፡ ቀኖች ፡ እንደ ፡ ፋር ፡
ስም ፡ ፋሪም ፡ ተባሉ ። በዚህም ፡ ደብዳቤ ፡
ስለ ፡ ተጻፈው ፡ ቃል ፡ ሁሉ ÷ ስላዩትና ፡ ስላገ
፳፯፳፰፤ ኙአቸውም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ÷ አይሁድ ፡ እነዚህን ፡
ሁለት ፡ ቀኖች ፡ እንደ ፡ ጽሕፈቱና ፡ እንደ ፡
ጊዜው ፡ በየዓመቱ ፡ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ÷ እነዚ
ህም ፡ ቀኖች ፡ በየትውልዳቸውና ፡ በየወገና
ቸው ፡ በየአገራቸውም ፡ በየከተማቸውም ፡ የታ
ሰቡና ፡ የተከበሩ ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ÷ እነዚህም ፡
የፋሪም ፡ ቀኖች ፡ በአይሁድ ፡ ዘንድ ፡ እንዳይ
ሻሩ ÷ መታሰቢያቸውም ፡ ከዘራቸው ፡ እንዳይቈ
ረጥ ÷ በራሳቸውና ፡ በዘራቸው ፡ ወደ ፡ እነር
ሱም ፡ በተጠጉት ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ እንዳይቀር ፡
ሥርዓት ፡ አድርገው ፡ ተቀበሉ ።
፳፱፤ የአቢካኢልም ፡ ልጅ ፡ ንግሥቲቱ ፡ አስቴርና ፡
አይሁዳዊው ፡ መርዶክዮስ ፡ ይህችን ፡ ስለ ፡
ፋሪም ፡ የምትናገረውን ፡ ሁለተኛይቱን ፡ ደብ
ዳቤ ፡ በሥልጣናቸው ፡ ሁሉ ፡ ያጸኑአት ፡ ዘንድ ፡
፴፤ ጻፉ ። ደብዳቤዎቹንም ፡ በአርጤክስስ ፡ መንግ
ሥት ፡ በመቶ ፡ ሀያ ፡ ሰባቱ ፡ አገሮች ፡ ወዳሉ ፡
አይሁድ ፡ ሁሉ ፡ በሰላምና ፡ በእውነት ፡ ቃል ፡
፴፩፤ ላኩ ። እነዚህንም ፡ የፋሪም ፡ ቀኖች ÷ አይሁ
ዳዊው ፡ መርዶክዮስና ፡ ንግሥቲቱ ፡ አስቴር ፡
እንዳዘዙ ÷ ለራሳቸውና ፡ ለዘራቸውም ፡ የጾማ
ቸውንና ፡ የልቅሶአቸውን ፡ ነገር ፡ ለማክበር ፡
እንደ ፡ ተቀበሉ ÷ በየጊዜያቸው ፡ ያጸኑ ፡ ዘንድ ፡
፴፪፤ ጻፉ ። የአስቴርም ፡ ትእዛዝ ፡ ይህን ፡ የፋሪምን ፡
ነገር ፡ አጸና ፤ በመጽሐፍም ፡ ተጻፈ ።

ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩፤ ንጉሡም ፡ አርጤክስስ ፡ በምድርና ፡ በባሕር ፡
፪፤ ደሴቶች ፡ ላይ ፡ ግብር ፡ ጣለ ። የኃይሉና ፡ የብ
ርታቱም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ንጉሡም ፡ እስከ ፡ ምን ፡
ድረስ ፡ እንዳከበረው ፡ የመርዶክዮስ ፡ ክብር ፡
ታላቅነት ÷ በሚዶንና ፡ በፋርስ ፡ ነገሥታት ፡
፫፤ ታሪክ ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈ ፡ አይደለምን ? አይ
ሁዳዊውም ፡ መርዶክዮስ ፡ ለንጉሡ ፡ ለአርጤ
ክስስ ፡ በማዕርግ ፡ ሁለተኛ ፡ ነበረ ፤ በአይሁድም ፡
ዘንድ ፡ የከበረ ÷ በብዙ ፡ ወንድሞችም ፡ ዘንድ ፡
የተወደደ ÷ ለሕዝቡም ፡ መልካምን ፡ የፈለገ ÷
ለዘሩም ፡ ሁሉ ፡ በደኅና ፡ የተናገረ ፡ ነበረ ።
መርዶክዮስም ፡— ይህ ፡ ነገር ፡ በእግዚአብ ፬፤
ሔር ፡ ፈቃድ ፡ ተደረገ ። የዚያ ፡ ሕልም ፡ ጊዜው ፡ ፭፤
አላለፈምና ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ያየሁት ፡ የሕል
ሚን ፡ ነገር ፡ አሰብሁ ፡ አለ ። ፈሳሽ ፡ የሆነች ፡ ፮፤
ያች ፡ ትንሽ ፡ የውኃ ፡ ምንጭ ÷ የዐሐይ ፡ ብር
ሃን ፡ የወጣላት ፡ ብዙው ፡ ውኃም ፡ የተገኘላት ÷
ንጉሥ ፡ ያገባት ፡ ንግሥትም ፡ ያደረጋት ፡ አስ
ቴር ፡ ናት ። እነዚያ ፡ ሁለቱም ፡ እባቦች ፡ ሐማና ፡ ፯፤
እኔ ፡ ነን ። የእስራኤልን ፡ ስም ፡ ያጠፉ ፡ ዘንድ ፡ ፰፤
የተሰበሰቡትም ፡ አሕዛብ ፡ ናቸው ። ወደ ፡ እግ ፱፤
ዚአብሔር ፡ የጮሁ ፡ ከመከራውም ፡ የዳኑ ፡
ወገኖቹ ፡ እስራኤል ፡ ናቸው ። እግዚአብሔር ፡
ወገኖቹን ፡ ከመከራው ፡ አዳናቸው ፤ እግዚአብ
ሔርም ፡ ከመከራው ፡ ሁሉ ፡ አዳነን ፤ እግዚአ
ብሔርም ፡ በሕዝቡ ፡ ዘንድ ፡ እንደዚህ ፡ ያልተ
ደረገ ፡ ብዙ ፡ ድንቅ ፡ ታምራትን ፡ አደረገ ።
ስለዚህም ፡ ነገር ፡ ሁለት ፡ ዕጣ ፡ አደረገ ፤ አንዱ ፡ ፲፤
ዕጣ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ወገኖች ፡ የእስራኤል ፡
ዕጣ ፡ ነው ÷ ሁለተኛውም ፡ ዕጣ ፡ የአሕዛብ ፡
ነው ፤ እኛም ፡ ዕጣዎች ፡ ቍርጥ ፡ ፍርድ ፡ በሚ ፲፩፤
ደረግበት ፡ ሰዓት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡
በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ደረሱ ። እግዚአብ ፲፪፤
ሔርም ፡ ወገኖቹ ፡ እስራኤልን ፡ አሰባቸው ÷
ማደሪያዎቹ ፡ እስራኤልንም ፡ ከኃጢአት ፡ አነ
ጻቸው ። እነዚያም ፡ ቀኖች ፡ እንደዚህ ፡ ሆኑ ፡ ፲፫፤
በአዳር ፡ ወር ፡ ይህ ፡ ወር ፡ በበተ ፡ በአሥራ ፡
አምስተኛውና ፡ በአሥራ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በተድላ ፡ በደስታ ፡ ተሰ
ብስበው ፡ ለዘላለሙ ፡ ባላ ፡ ዘመናቸው ፡ በወገ
ኖቹ ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ የሚ
ያደርጉባቸው ፡ ሆኑ ።

ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

ጰጠሎሚዎስና ፡ ቀለዮጳጥራ ፡ በነገሡ ፡ በአ
ራተኛው ፡ ዓመት ÷ ካህንና ፡ ሌዊ ፡ ነኝ ፡ ያለው ፡
ዘሲጠዮስና ፡ ልጁ ፡ ጰጠሎሚዎስ ÷ በኢየሩሳ
ሌም ፡ ከሚኖሩት ፡ አንዱ ፡ የጰጠሎሚዎስ ፡
ልጅ ፡ ሊሲማኮስ ፡ ተረጎማት ፡ ያሏትን ፡ የፋሪ
ምን ፡ መልእክት ፡ አመጡ ።

# መጽሐፈ ፡ መቃብያን ፡ ቀዳማዊ ።

በሞዓባውያንና ፡ በሚዶናውያን ፡ መንግሥት ፡ መቃብያን ፡ የተናገሩት ፡ ነገር ፡ ይህ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ ስሙ ፡ ጺሩጻይዳን ፡ የሚባል ፡ ኃጢአትንም ፡
የሚወዳት ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ነበር ፡ በፈረሶቹ ፡
ብዛት ፡ ከሥልጣኑ ፡ በታች ፡ በጭፍራዎቹም ፡
ጽናት ፡ ይመካ ፡ ነበር ።
፪፤ የሚያመልካቸውና ፡ የሚሰግድላቸው ፡ በሌ
ሊት ፡ በመዓልትም ፡ መሥዋዕት ፡ የሚሠዋላ
ቸው ፡ ጣዖታቱን ፡ የሚያገለግሉ ፡ ብዙ ፡ ካህ
ናት ፡ ነበሩት ።
፫፤ እሱ ፡ ግን ፡ በልቡናው ፡ ድንቁርና ፡ እነሳቸው ፡
ጽናትና ፡ ኃይልን ፡ የሚሰጡት ፡ ይመስለው ፡
ነበር ።
፬፤ በልቡም ፡ በግዛቱ ፡ ሁሉ ፡ እነሳቸው ፡ ሥልጣ
ንን ፡ የሚሰጡት ፡ ይመስለው ፡ ነበር ።
፭፤ ዳግመኛም ፡ በሰልፍ ፡ ጊዜ ፡ እነሳቸው ፡ የተመ
ኘውንም ፡ ሁሉ ፡ ሥልጣን ፡ የሚሰጡት ፡ ይመ
ስለው ፡ ነበር ።
፮፤ እርሱም ፡ ቀንና ፡ ሌሊት ፡ መሥዋዕት ፡ ይሠዋ
ላቸው ፡ ነበር ።
፯፤ ጣዖታቱን ፡ የሚያገለግሉ ፡ ካህናትን ፡ ሾመ ።
፰፤ ከዚያች ፡ ከረከሰች ፡ መሥዋዕት ፡ እነሳቸው ፡
እየበሉ ፡ ሌሊትና ፡ ቀን ፡ ጣዖቶቹ ፡ የሚበሉ ፡
አስመስለው ፡ ይነግሩት ፡ ነበር ።
፱፤ ዳግመኛ ፡ መሥዋዕት ፡ ሠውተው ፡ ይበሉ ፡
ዘንድ ፡ ሌሎች ፡ ሰዎችን ፡ እንደነሳቸው ፡ ያተጉ ፡
ነበረ ። ዳግመኛም ፡ እነሳቸው ፡ መሥዋዕት ፡
ሠውተው ፡ እንደነሳቸው ፡ መሥዋዕት ፡ ይሠዉ ፡
ዘንድ ፡ ሌሎች ፡ ሰዎችን ፡ ያተጉ ፡ ነበር ።
፲፤ እሱ ፡ ግን ፡ በማይረባ ፡ በማይጠቅም ፡ ጣዖት ፡
ይታመን ፡ ነበር ።
፲፩፤ በውቀቱ ፡ ማነስና ፡ በልቡ ፡ ድንቁርና ፡ የፈጠ
ሩት ፡ እነሳቸው ፡ የሚመግቡት ፡ እነሳቸውም ፡
የሚያነግሡት ፡ ይመስለው ፡ ነበር ፡ ካለመኖር ፡
ወደ ፡ መኖር ፡ አምጥቶ ፡ በነፍስ ፡ በሥጋ ፡
የፈጠረው ፡ ፈጣሪውን ፡ እንዳያውቅ ፡ አማል
ክት ፡ ሳይሆኑ ፡ አማልክት ፡ ካላቸው ፡ ከሱ ፡
ጋራ ፡ ተፈርዶባቸው ፡ ለዘለዓለም ፡ ወደ ፡ ገሃ
ነመ ፡ እሳት ፡ ይሄዱ ፡ ዘንድ ፡ ካለመኖር ፡ ወደ ፡
መኖር ፡ አምጥቶ ፡ የፈጠረውን ፡ ፈጣሪውን ፡
እሱ ፡ ከወገኖቹ ፡ ጋራ ፡ እንዳያውቅ ፡ ሰይጣን ፡
ልቡናውን ፡ አደንቁሮታልና ፡ የፈጠሩት ፡ ይመ
ስለው ፡ ነበር ።
፲፪፤ መቼም ፡ መቼም ፡ ደኅኖች ፡ አይደሉምና ፡
ሙታን ፡ ይላቸው ፡ ዘንድ ፡ ይገባል ።
፲፫፤ የሚያስታቸው ፡ የሰይጣን ፡ ሥልጣን ፡ በዚያ ፡
በጣዖቱ ፡ ምስል ፡ ያድራልና ፡ የልቡናቸውንም ፡
ፈቃድ ፡ ይነግራቸዋልና ፡ እንደ ፡ ወደዱም ፡ ይገ
ልጥላቸዋልና ፡ ባመኑባቸው ፡ ልቡናቸውም ፡
እንደ ፡ አመድ ፡ የሆነ ፡ የአዳም ፡ ልጆች ፡ በሚ
ታመኑባቸው ፡ በጣዖቶቹ ፡ ይፈረድባቸዋል ።
ያሰቡትንም ፡ እንደ ፡ ፈጻመላቸው ፡ በዩ ፡ ጊዜ ፡ ፲፬፤
ያደንቃሉ ፡ እነርሳቸውም ፡ ከበሕርያቸው ፡ የተ
ወለዱ ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻቸውንና ፡ ወንዶች ፡ ልጆ
ቻቸውን ፡ እስኪሠዉ ፡ ንጹሕ ፡ የሆነ ፡ የሴቶች ፡
ልጆቻቸውንና ፡ የወንዶች ፡ ልጆቻቸውን ፡ ደም ፡
እስኪያፈሱ ፡ ድረስ ፡ ደርሰው ፡ ፈቃዱን ፡ ያደ
ርጉለታል ።
እስከ ፡ ዘለዓለም ፡ ድረስ ፡ መውጫ ፡ ወደ ፡ ሌለ ፡ ፲፭፤
በት ፡ እሱ ፡ መከራ ፡ ወደሚቀበልበት ፡ እንደሱ ፡
ወደ ፡ ገሃነም ፡ ያወርዳቸው ፡ ዘንድ ፡ ሰይጣን ፡
ክፉ ፡ ፈቃዳቸውን ፡ ለመፈጸም ፡ መሥዋዕቱን ፡
አጣጥሞላቸዋልና ፡ አላሳዘኗቸውም ።
ያ ፡ ጺሩጻይዳን ፡ ግን ፡ ትዕቢተኛ ፡ ነበር ፡ በወን ፡ ፲፮፤
ዶች ፡ አምሳል ፡ የተሠሩ ፡ አምሳ ፡ በሴቶች ፡
አምሳል ፡ የተሠሩ ፡ ኻያ ፡ ጣዖቶች ፡ ነበሩት ።
ጥቅም ፡ በሌላቸው ፡ በነዚያ ፡ በጣዖታቱም ፡ ፲፯፤
ይመካ ፡ ነበር ፡ ጧትና ፡ ማታ ፡ መሥዋዕት ፡ እየ
ሠዋ ፡ ፈጽሞ ፡ ያከብራቸው ፡ ነበር ።
ሰዎችንም ፡ ለጣዖቱ ፡ መሥዋዕት ፡ ይሠዉ ፡ ፲፰፤
ዘንድ ፡ ያዛቸው ፡ ነበር ፡ እሱም ፡ ከዚያች ፡ ከረ
ከሰች ፡ መሥዋዕት ፡ ይበላ ፡ ነበር ፡ ከመሥዋዕቱ ፡
ይበሉ ፡ ዘንድ ፡ ሌሎችንም ፡ ሰዎች ፡ ያዛቸው ፡
ነበር ፡ ይልቁንም ፡ ለክፉት ፡ ይተናከል ፡ ነበር ።
የብረትና ፡ የናስ ፡ የእርሳስም ፡ ለሆኑ ፡ ተመት ፡ ፲፱፤
ተው ፡ ለተሠሩ ፡ ጣዖታቱ ፡ አምስት ፡ ቤት ፡ አሠ
ራላቸው ።
በብርና ፡ በወርቅም ፡ አስጌጣቸው ፡ በቤቱ ፡ ፳፤
ዙሪያ ፡ መጋረጃ ፡ አስጋረደላቸው ፡ ድንኳንም ፡
አስተከለላቸው ።
በዚያ ፡ ጠባቂዎችን ፡ ሾመላቸው ፡ የሰቡ ፡ ፳፩፤
አሥር ፡ በሬችን ፡ አሥር ፡ መሲናዎች ፡ ላሞ
ችን ፡ የሰቡ ፡ አሥር ፡ የበግ ፡ ሙክቶችን ፡ የመ
ሰኑ ፡ አሥር ፡ ፍየሎችን ፡ ክንፍ ፡ ካላቸው ፡ ከወ
ፎች ፡ ጋራ ፡ ለጣዖታቱ ፡ ዘወትር ፡ ዓርባ ፡ ይሠ
ዋላቸው ፡ ነበር ።
ለሱ ፡ ግን ፡ ጣዖታቱ ፡ የሚበሉ ፡ ይመስለው ፡ ፳፪፤
ነበር ፡ አምሳ ፡ ፊቀን ፡ ወይን ፡ በዘይት ፡ የታሸ ፡
አምሳ ፡ ወጪት ፡ ስንዴን ፡ ያቀርብላቸው ፡
ነበር ።
ካህናቱንም ፡ ወስዳችሁ ፡ ስጡቸው ፡ ፈጣሪዎቹ ፡ ፳፫፤
ያረድሁላቸውን ፡ ሥጋ ፡ ይብሉ ፡ ያቀረብሁላቸ
ውንም ፡ ወይን ፡ ይጠጡ ፡ ባይበቃቸውም ፡ እኔ ፡
እጨምርላቸዋለሁ ፡ አላቸው ።
ከዚያች ፡ ከረከሰች ፡ መሥዋዕትም ፡ ይበሉ ፡ ፳፬፤
ይጠጡ ፡ ዘንድ ፡ ሁሉን ፡ ያዝዝ ፡ ነበር ።

፳፭ እሱ ፡ ግን ፡ በክፉ ፡ ትንኰሉ ፡ የማይሠዋም ፡ የማይሰግድም ፡ እንዳለ ፡ ለይተው ፡ አውቀው ፡ ያመጡት ፡ ዘንድ ፡ በራቱም ፡ በእሳትና ፡ በሰይፍ ፡ ይቀጡት ፡ ዘንድ ፡ ገንዘቡን ፡ ይበረብሩት ፡ ዘንድ ፡ ቤቱንም ፡ በእሳት ፡ ያቃጥሉት ፡ ዘንድ ፡ ያለውን ፡ ገንዘቡን ፡ ሁሉ ፡ ይወስዱበት ፡ ዘንድ ፡ በግዛቱ ፡ ሁሉ ፡ የሚገኙ ፡ ጭፍራዎቹን ፡ ላከ ።

፳፮ እነሳቸው ፡ ደጋጎችና ፡ ታላላቆች ፡ ናቸውና ፡ በቸርነታቸውም ፡ እኛን ፡ ፈጥረዋልና ፡ ፈጣሪዎቹን ፡ ከላመለከ ፡ ለፈጣሪዎቹ ፡ መሥዋዕት ፡ ከልሠዋ ፡ ለርሱም ፡ እኔ ፡ ቅጣትና ፡ መከራን ፡ አሳየዋለሁ ።

፳፯ ምድርና ፡ ሰማይን ፡ ሰሌ ፡ የሆነ ፡ ባሕርንም ፡ ጨረቃና ፡ ፀሐይንም ፡ ከዋክብትንም ፡ ዝናማትንና ፡ ነፋሳትንም ፡ ለኛ ፡ ምግብ ፡ ሊሆን ፡ ጽጋብም ፡ ሊሆነን ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ የሚኖረውንም ፡ ፈጥረዋልና ፡ እሱንም ፡ እኔ ፡ ቅጣትና ፡ መከራን ፡ አሳየዋለሁ ።

፳፰ የማያመልኳቸው ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ በፍጹም ፡ መከራ ፡ ይቀጣሉ ፡ አይራሩላቸውም ።

ምዕራፍ ፡ ፪ ።

፩ ከነገደ ፡ ብንያም ፡ የተወለደ ፡ ስሙ ፡ መቃቢስ ፡ የሚባል ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ነበረ ፤

፪ መልከ ፡ መልካም ፡ ፈጽመውም ፡ አርበኞች ፡ የሆኑ ፡ ሦስት ፡ ልጆች ፡ ነበሩት ፡ በሰው ፡ ሁሉ ፡ ዘንድ ፡ በዚያች ፡ በጺሩጺይዳን ፡ ግዛት ፡ የምትሆን ፡ በምድያምና ፡ በሜዶን ፡ አገር ፡ መወደድ ፡ ነበራቸው ።

፫ ባገኛቸውም ፡ ጊዜ ፡ ንጉሡ ፡ እንዳዘዘ ፡ ለጺሩጺይዳን ፡ ፈጣሪዎች ፡ አትሰግዱምን ፡ መሥዋዕትስ ፡ አትሠዉምን ።

፬ እምቢ ፡ ብትሉ ፡ ግን ፡ ይዘን ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ እንወስዳችኋለን ፡ ንጉሡም ፡ እንዳዘዘ ፡ ገንዘባችሁን ፡ ሁሉ ፡ እናጠፋለን ።

፭ መልከ ፡ መልካም ፡ የሆኑ ፡ እነዚያ ፡ ጕልማሶች ፡ እኛስ ፡ የምንሰግድለት ፡ ምድርና ፡ ሰማይን ፡ በውስጢ ፡ ያለውንና ፡ ባሕርንም ፡ ጨረቃንና ፡ ፀሐይን ፡ ደመናትና ፡ ከዋክብትንም ፡ የፈጠረ ፡ ያባታችን ፡ ፈጣሪ ፡ አለ ፡ እኛ ፡ የምናመልከው ፡ የምናምንበትም ፡ እውነተኛ ፡ ፈጣሪ ፡ እርሱ ፡ ነው ፡ ብለው ፡ መለሱለት ።

፮ እነዚህም ፡ የንጉሡ ፡ ብላቴኖች ፡ አራት ፡ ናቸው ፡ ጋሻ ፡ ጦራቸውን ፡ የሚሸከሙ፡ አሽከሮቻቸውም ፡ መቶ ፡ ናቸው ።

፯ እለዚህንም ፡ ቅዱሳን ፡ ይይዟቸው ፡ ዘንድ ፡ በወደዱ ፡ ጊዜ ፡ ከኛቸው ፡ አመለጡ ፡ የነከቸውም ፡ የለም ፡ እነዚያ ፡ ጕልማሶች ፡ በኃይል ፡ ፈጽሞ ፡ አርበኞች ፡ ናቸውና ፡ ጋሻ ፡ ጦራቸውን ፡ ይዘው ፡ ሄዱ ።

፰ ከነርሳቸውም ፡ አንቆ ፡ ግስላ ፡ የሚገድል ፡ ነበር ፡ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ እንደ ፡ ዶሮ ፡ ያንቀው ፡ ነበር ።

፱ ከነርሳቸውም ፡ ባንዲት ፡ ደንጊያ ፡ ወይም ፡ ባንድ ፡ ጊዜ ፡ በበትር ፡ መትቶ ፡ አንበሳ ፡ የሚገድል ፡ ነበር ።

፲ ከነርሳቸውም ፡ በሰልፍ ፡ ጊዜ ፡ ባንድ ፡ ሰይፍ ፡ መትቶ ፡ መቶ ፡ ሰው ፡ የሚገድል ፡ ነበር ፡ ስማቸው ፡ አደናቸውም ፡ እንዲህ ፡ ነበር ፡ በባቢሎንና ፡ በምዕብ ፡ አገር ፡ ሁሉ ፡ የተጠራ ፡ ነበር ።

፲፩ በኃይልም ፡ አርበኞች ፡ ነበሩ ፡ የነገር ፡ መወደድና ፡ ደም ፡ ግባትም ፡ ነበራቸው ።

፲፪ ዳግመኛም ፡ የመልካቸው ፡ ደም ፡ ግባት ፡ ድንቅ ፡ ነበር ፡ ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ስላመለኩት ፡ ሞትንም ፡ ስላልፈሩት ፡ ከሁሉ ፡ የምትበልጥ ፡ የልቡናቸው ፡ ደም ፡ ግባት ፡ ናት ።

፲፫ ጭፍራዎችንም ፡ በስፈሩዋቸው ፡ ጊዜ ፡ ይይዟቸው ፡ ዘንድ ፡ የቻለ ፡ የለም ፡ አርበኞች ፡ የሆኑ ፡ እነርሳቸው ፡ ግን ፡ ከፍ ፡ ወዳለ ፡ ተራራ ፡ ወጥተው ፡ አመለጡ ።

፲፬ እነዚያም ፡ ጭፍሮች ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ ተመልሰው ፡ ያምባውን ፡ በር ፡ ዘጉ ፡ እነዚያን ፡ አርበኞች ፡ መቃብያንን ፡ ካላመጣችኋቸው ፡ ከተማችሁን ፡ በእሳት ፡ እናቃጥላታለን ፡ ወደ ፡ ንጉሡም ፡ ልከን ፡ አገራችሁን ፡ እናጠፋለን ፡ ብለው ፡ ሕዝቡን ፡ አስፈራሯቸው ።

፲፭ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ያገሩ ፡ ሰዎች ፡ ባለጸጎችና ፡ ድሆች ፡ ሴቶችና ፡ ወንዶችም ፡ እናት ፡ አባቱ ፡ የሞቱበት ፡ ልጅና ፡ ባልቴቶችም ፡ ሁሉም ፡ ወጥተው ፡ አንድነት ፡ ጮሁ ፡ እንገታቸውንም ፡ ወደ ፡ ተራራ ፡ አቀኑ ፡ እኛን ፡ አታጥፉን ፡ አገራችንንም ፡ አታጥፉብን ፡ ብለው ፡ ወደነሳቸው ፡ ጮሁ ።

፲፮ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ አንድነት ፡ አለቀሱ ፡ ከእግዚአብሔርም ፡ የተነሣ ፡ ፈሩ ።

፲፯ ፊታቸውን ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ መልሰው ፡ እጃቸውንም ፡ ዘርግተው ፡ አንድነት ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለመኑ ፡ አቤቱ ፡ ትእዛዝህንና ፡ ሕግህን ፡ ያፈረሱ ፡ እነዚህን ፡ ሰዎች ፡ እንቢ ፡ እንበላቸውን ።

፲፰ በብርና ፡ በወርቅ ፡ የሰው ፡ እጅ ፡ በሠራው ፡ በደንጊያና ፡ በእንጨት ፡ አመነ ፡ እንጂ ፡ እኛ ፡ ግን ፡ ሕግህን ፡ ያላመነ ፡ የዚያን ፡ የወንጀለኛ ፡ ቃል ፡ እንሰማ ፡ ዘንድ ፡ አንወድም ፡ አሉ ።

፲፱ የምታድንና ፡ የምትገድል ፡ አንተ ፡ ፈጣሪው ፡ ሳለህ ፡ ራሱንም ፡ እነርሱ ፡ እንደፈጠሩት ፡ ያደርጋል ፡ እርሱስ ፡ የሰውን ፡ ደም ፡ የሚያፈስ ፡ የሰውንም ፡ ሥጋ ፡ የሚበላ ፡ ነው ።

፳ እኛ ፡ ግን ፡ የዚያን ፡ የወንጀለኛ ፡ ፊት ፡ እናይ ፡ ዘንድ ፡ ቃሉንም ፡ እንሰማ ፡ ዘንድ ፡ አንወድም ፡ አሉ ።

፳፩ ነገር ፡ ግን ፡ አንተ ፡ ከዘገከን ፡ ወደሱ ፡ እንሄዳለን ፡ ባንተ ፡ ስላመን ፡ ሰውነታችንን ፡ ለሞት ፡ አሳልፈን ፡ እንሰጣለን ፡ ለፈጣሪዎቹ ፡ መሥዋዕት ፡ ሠዉ ፡ ባለ ፡ ጊዜም ፡ የዚያን ፡ የወንጀለኛ ፡ ቃል ፡ አንሰማም ።

፳፪ ፈቃድህን ፡ ያደረጉ ፡ በሕግህም ፡ ጸንተው ፡ የኖሩ ፡ ቸላሊትና ፡ ልቡናንም ፡ የምትመረምር ፡ አቤቱ ፡ የአባቶቻችን ፡ የአብርሃም ፡ የይስሐቅ ፡

የያዕቆብ ፡ ፈጣሪ ፡ እኛ ፡ ግን ፡ እንተን ፡ እመን ።
፳፫ የሰው ፡ ልቡና ፡ መርምረህ ፡ ኃጥኡንና ፡ ጻድ
ቁን ፡ ትረዳዋለህ ፡ የሚሠወርህም ፡ የለ ፡ የተሸ
ሸገውም ፡ በንተ ፡ ዘንድ ፡ የተገለጠ ፡ ነው ።
፳፬ እኛ ፡ ግን ፡ ከንተ ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ ፈጣሬ ፡ የለንም ።
፳፭ ስለ ፡ ከበረ ፡ ስምህ ፡ ሰውነታችንን ፡ ለሞት ፡
እንሰጥ ፡ ዘንድ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ በዚህ ፡ በምንገዛ
ልህ ፡ ሥራ ፡ ኃይልን ፡ ጽናትን ፡ መጠጊያን ፡
ሁነን ።
፳፮ እስራኤልም ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ አገር ፡ በገቡ ፡ ጊዜ ፡
የያዕቆብን ፡ ልመና ፡ ሰማህ ፡ አሁንም ፡ የከበ
ርህ ፡ አምላክ ፡ እንለምንሃለን ።
፳፯ መልካቸው ፡ ፈጽሞ ፡ ያማረ ፡ ሁለቱም ፡ ሰዎች ፡
በፊታቸው ፡ ቁመው ፡ በታይዋቸው ፡ ጊዜ ፡
እንደ ፡ መብረቅ ፡ የሚያስፈሩ ፡ የእሳት ፡ ሰይ
ፎች ፡ ወርደው ፡ አንገታቸውን ፡ ቆርጠው ፡ በገ
ደሏቸው ፡ ጊዜ ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ቀደመው ፡
ደኅነኞች ፡ ሁነው ፡ ተነሡ ።
፳፰ የመልካቸው ፡ ደም ፡ ግባት ፡ ፈጽሞ ፡ ያማረ ፡
ሆነ ፡ ከፀሐይም ፡ ይልቅ ፡ አበሩ ፡ ከቀደመውም ፡
ይልቅ ፡ ያማሩ ፡ ሆኑ ።

ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ የልዑል ፡ የእግዚአብሔር ፡ ባሮች ፡ አብያ ፡
ሲላ ፡ ፈንቶስ ፡ ሞተው ፡ የተነሡ ፡ እነዚህን ፡
በፊታችሁ ፡ እንዳያችሁ ፡ ከሞታችሁ ፡ በኋላ ፡
እንደዚሁ ፡ ትነሣ ፡ ዘንድ ፡ አላችሁ ፡ ፊታች
ሁም ፡ በመንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ እንደ ፡ ፀሐይ ፡
ይበራል ።
፪ ከነዚያ ፡ ሰዎችም ፡ ጋራ ፡ ሂደው ፡ በዚያ ፡ ሰማ
ዕትነትን ፡ ተቀበሉ ።
፫ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ለመኑ ፡ አመሰገኑ ፡ ለእግዚአብ
ሔርም ፡ ሰገዱ ፡ ሞት ፡ አላስፈራቸውም ፡ የን
ጉሡም ፡ ቅጣት ፡ አላስፈራቸውም ።
፬ ወደነዚያ ፡ ብላቴኖችም ፡ ሄዱ ፡ ክፉት ፡ እንደ
ሌለው ፡ በግ ፡ ሆኑ ፡ እንጂ ፡ አላስፈሩዋቸውም ፡
ወደነሱም ፡ በደረሱ ፡ ጊዜ ፡ ይዘው ፡ መቷቸው ፡
አሥረውም ፡ ገረፏቸው ፡ ወደ ፡ ንጉሡም ፡
አድርሰው ፡ በፊቱ ፡ አቆሟቸው ።
፭ ንጉሡም ፡ እናንተ ፡ እምቢተኞች ፡ ለፈጣሪዎቼ ፡
መሥዋዕት ፡ ሠውታችሁ ፡ እንዴት ፡ አትሰግ
ዱላቸውም ፡ ብሎ ፡ መለሰላቸው ።
፮ ከኃጢአት ፡ የነጹ ፡ የከበሩ ፡ የተመረጡ ፡ ደስ ፡
ያላቸው ፡ ዋጋው ፡ ድንቅ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እንደ ፡ ዕን
ቍም ፡ የሚያበሩ ፡ እነዚያ ፡ ወንድማማቾች ፡
ሲላና ፡ አብያ ፡ ፈንቶስም ፡ በንድ ፡ ቃል ፡ መለ
ሱለት ።
፯ ቻነፈር ፡ የሆነ ፡ ያንን ፡ ንጉሥ ፡ እኛስ ፡ ዕውቀ
ትና ፡ ልቡና ፡ ለሌላቸው ፡ ለረከሱ ፡ ጣዖቶች ፡
አንሰግድም ፡ አንሠዋም ፡ አሉት ።
፰ ዳግመኛም ፡ ብርና ፡ ወርቅ ፡ የሰው ፡ እጅ ፡ ለሠ
ራቸው ፡ ድንጋይና ፡ እንጨት ፡ ለሆኑ ፡ ልቡናና ፡
ነፍስ ፡ እውቀትም ፡ ለሌላቸው ፡ ወዳጃቸውን ፡
ለማይጠቅሙ ፡ ጠላቶቻቸውንም ፡ ለማይገዱ ፡
ጣዖታት ፡ አንሰግድም ፡ አሉት ።
ንጉሡም ፡ እንዲህ ፡ ለምን ፡ ታደርጋላችሁ ፡ ፱
እነሱም ፡ የሚሰድቡቸውንና ፡ የሚበድላቸውን ፡
ያውቃሉና ፡ የከበሩ ፡ የሆኑ ፡ ፈጣሪዎችን ፡
ለምን ፡ ትሰድባላችሁ ፡ ብሎ ፡ መለሰላቸው ።
እነርሱ ፡ በእኛ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ኢምንት ፡ ናቸ ፲
ውና ፡ እኛስ ፡ እንሰድባቸዋለን ፡ አናከብራቸ
ውም ፡ ብለው ፡ መለሱለት ።
ንጉሡም ፡ እንደሥራችሁ ፡ ክፉት ፡ መጠን ፡ ፲፩
እቀጣችኋለሁ ፡ በግርፋትና ፡ በጽኑ ፡ መከራ ፡
በእሳትም ፡ የመልካችሁን ፡ ደም ፡ ግባት ፡ አጠ
ፋለሁ ።
አሁንም ፡ ለፈጣሪዎቼ ፡ መሥዋዕት ፡ ትሰጡ ፡ ፲፪
እንደ ፡ ሆነ ፡ ወይም ፡ አትሰጡ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
ንገሩኝ ፡ ይህስ ፡ ካልሆነ ፡ በሰይፍ ፡ በግርፋት ፡
እቀጣችኋለሁ ፡ ብሎ ፡ መለሰላቸው ።
እኛስ ፡ ለረከሱ ፡ ጣዖታት ፡ መሥዋዕት ፡ አንሠ ፲፫
ዋም ፡ አንሰግድም ፡ ብለው ፡ መለሱለት ፡ ንጉ
ሡም ፡ በወፍራም ፡ በትር ፡ ይመቷቸው ፡ ዘንድ ፡
ዳግመኛም ፡ በጅራፍ ፡ ይገርፏቸው ፡ ዘንድ ፡
ከሱም ፡ በኋላ ፡ ውስጥ ፡ እካላቸው ፡ እስኪታይ ፡
ድረስ ፡ ይሰነጥቋቸው ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ።
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በሚቀጣቸው ፡ በሚገድላቸው ፡ ፲፬
ገንዘብ ፡ እስኪመክር ፡ ድረስ ፡ አሥረው ፡ በግ
ዞት ፡ ቤት ፡ አዋሏቸው ።
ወስደው ፡ ያለ ፡ ርኅራኄ ፡ በእሥር ፡ ቤት ፡ ጽኑ ፡ ፲፭
እሥራትን ፡ አሠሩዋቸው ፡ እነርሱም ፡ በእሥር ፡
ቤት ፡ ሦስት ፡ ሌሊትና ፡ ሦስት ፡ መዓልት ፡ ተቀ
መጡ ።
ከዚህ ፡ ከሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ንጉሡ ፡ ፲፮
አዋጅ ፡ ነጋሪ ፡ ይዞር ፡ ዘንድ ፡ መከሮችና ፡ መኳ
ንንቶች ፡ ያገር ፡ ሽማግሎችና ፡ ሹማምንቱ ፡ ይሰ
በሰቡ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ።
ንጉሡ ፡ ጺሩጻይዳንም ፡ በደበባይ ፡ በተቀመጠ ፡ ፲፯
ጊዜ ፡ እነዚያን ፡ የከበሩ ፡ ሲላና ፡ አብያን ፡ ፈን
ቶስንም ፡ ያመጧቸው ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፡ የቆሰ
ሉና ፡ የታሠሩ ፡ ሁነው ፡ በፊቱ ፡ ቆሙ ።
ንጉሡም ፡ ይኸንን ፡ ሦስቱን ፡ ቀን ፡ ስትቀመጡ ፡ ፲፰
በውኑ ፡ የተመለሳችሁት ፡ መመለስ ፡ አለን ፡
ወይስ ፡ እናንተ ፡ በቀደመው ፡ ክፉታችሁ ፡ አላ
ችሁን ፡ አላቸው ።
የከበሩ ፡ እነዚያ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ጭፍራዎ ፲፱
ችም ፡ እኛስ ፡ የጨከንን ፡ ኃጢአትና ፡ ክፉትን ፡
የተመላ ፡ አንተ ፡ የምታመልከውን ፡ ጣዖትን ፡
እናመልክ ፡ ዘንድ ፡ እሺ ፡ አንልም ፡ ብለው ፡
መለሱለት ።
ያም ፡ ወንጀለኛ ፡ ተቆጥቶ ፡ ከፍ ፡ ባለ ፡ በታ ፡ ፳
ያቆሟቸው ፡ ዘንድ ፡ ቍስላቸውንም ፡ ያድሱት ፡
ዘንድ ፡ አዘዘ ፡ ደማቸው ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ፈሰሰ ።
ዳግመኛም ፡ በጭራሮ ፡ መብራት ፡ ያቃጥሏ ፳፩
ቸው ፡ ዘንድ ፡ ሥጋቸውም ፡ ያር ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፡
አሽከሮቹም ፡ እንዳዘዛቸው ፡ አደረጉ ፡ እነዚ
ያም ፡ የከበሩ ፡ ሰዎች ፡ ሕገ ፡ እግዚአብሔርን ፡
የዘነጋህ ፡ አንተ ፡ ተናገር ፡ ቅጣታችንን ፡ በምታ

በዛብን ፡ መጠን ፡ ዋጋችን ፡ ይበዛል ፡ አሉት ።
፳፪ ዳግመኛም ፡ ሥጋቸውን ፡ ከአጥንታቸው ፡ ጋራ ፡
ፈጽመው ፡ ይበሏቸው ፡ ዘንድ ፡ ምግባቸውን ፡
ሳይበሉ ፡ ክፉ ፡ አውሬዎች ፡ የሆኑ ፡ ድብና ፡
ነብር ፡ አንበሳም ፡ አምጥተው ፡ ይሰዱባቸው ፡
ዘንድ ፡ አዘዘ ።
፳፫ አውሬዎች ፡ የሚጠብቁ ፡ ሰዎችንም ፡ አውሬዎ
ቹን ፡ ይሰዱባቸው ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፡ እነርሱቸውም ፡
እንዳዘዛቸው ፡ አደረጉ ፡ የከበሩ ፡ እነዚያን ፡ ሰማ
ዕታትንም ፡ የማርማሪት ፡ አሥሩዋቸው ፡ ዳግመ
ኛም ፡ ተተንኩለው ፡ ከስማ ፡ መትተው ፡ አሥ
ሩዋቸው ።
፳፬ እነዚያም ፡ አውሬዎች ፡ እያንዳንዱ ፡ በላያቸው ፡
ተወረወሩ ፡ ወደ ፡ ሰማዕታቱም ፡ በደረሱ ፡ ጊዜ ፡
እጅ ፡ ነሥተው ፡ ሰገዱላቸው ።
፳፭ እያንዳንዱ ፡ ወደ ፡ ጠባቂዎቻቸው ፡ ተመለሱ ፡ ጠባ
ቂዎቻቸውንም ፡ አስፈሯቸው ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡
ፊት ፡ እስኪያደርሷቸው ፡ ድረስ ፡ ወደ ፡ አደባ
ባይ ፡ ወሰዷቸው ።
፳፮ በዚያም ፡ ከወንጀለኞች ፡ ሠራዊት ፡ ሰባ ፡ አም
ስት ፡ ሰዎች ፡ ገደሉ ።
፳፯ ንጉሡ ፡ ዙፋኑን ፡ ትቶ ፡ እስኪሸሽ ፡ ድረስ ፡
በፍርሃት ፡ አንዱ ፡ ባንዱ ፡ ላይ ፡ ተጨናንቀው ፡
ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ተሸበሩ ፡ አውሬዎቹንም ፡ በጭ
ንቅ ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡ ማደሪያቸው ፡ ወሰዱዋ
ቸው ።
፳፰ የሲላና ፡ የአብያ ፡ የፊንቶስ ፡ ሁለቱ ፡ ወንድሞ
ቻቸው ፡ መጥተው ፡ ከሥሩዋቸው ፡ አሥራት ፡
ፈትተው ፡ እነዚህ ፡ ተጠራጣሪና ፡ ወንጀለኞች ፡
እንዳያገኙን ፡ ኑ ፡ እንሽሽ ፡ አሏቸው ።
፳፱ እነዚያም ፡ ሰማዕታት ፡ ወንድሞቻቸውን ፡ ለም
ስክርናት ፡ ከቆምን ፡ በኋላ ፡ እንሽሽ ፡ ዘንድ ፡ አገ
ባብ ፡ አይደለም ፡ እናንተ ፡ ፈርታችሁ ፡ እንደ ፡
ሆነ ፡ ሸሽታችሁ ፡ ሂዱ ፡ ብለው ፡ መለሱላቸው ።
፴ እነዚያም ፡ ታናናሽ ፡ ወንድሞቻቸው ፡ እኛም ፡
በንጉሡ ፡ ፊት ፡ ከናንተ ፡ ጋራ ፡ እንቆማለን ፡
ብትሞቱም ፡ እኛ ፡ አብረን ፡ እንሞታለን ፡ አሉ ።
፴፩ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ንጉሡ ፡ በጌትነቱ ፡ አዳራሽ ፡
ሰገነት ፡ ላይ ፡ ሁኖ ፡ እነዚህ ፡ የከበሩ ፡ ሰዎች ፡
እንደተፈቱ ፡ አምስቱም ፡ ወንድማማቾች ፡
ሁሉ ፡ አንድነት ፡ እንደቆሙ ፡ አየ ፡ ጭፍራዎ
ችን ፡ የሚሠሩ ፡ የሚቀጡ ፡ እነዚያ ፡ አለቆች ፡
ወንድሞቻቸው ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ ጠይቀው ፡ ለን
ጉሡ ፡ ነገሩት ፡ ንጉሡም ፡ ቲቆጥቶ ፡ እንደ ፡
ምድረ ፡ በዳ ፡ አሪያ ፡ ሮኸ ።
፴፪ ንጉሡም ፡ አምስቱን ፡ ወንድማማቾች ፡ ሁሉ ፡
በሚቀጣቸው ፡ ገንዘብ ፡ እስኪመክር ፡ ድረስ ፡
ይዘው ፡ በእሥር ፡ ቤት ፡ ይጨምሩዋቸው ፡
ዘንድ ፡ አዘዘ ፡ በተፈለፈለ ፡ ግንድ ፡ ያለ ፡ ርኅ
ራኄ ፡ ጽኑ ፡ እሥራትን ፡ አሥረው ፡ በእሥር ፡
ቤት ፡ አኖሯቸው ።
፴፫ ንጉሡ ፡ ጲሩጳይዳንም ፡ እለዚህ ፡ የሳቱ ፡ ጎል
ማሶች ፡ አደከሙኝ ፡ የነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ልቡና
ቸው ፡ ምን ፡ ይጸና ፡ የሥራቸውም ፡ ክፋት ፡
እንደ ፡ ኃይላቸው ፡ ጽናት ፡ ነው ፡ ይመስላሉ ፡
ብሎ ፡ ልቡናቸውን ፡ ያከፋሉ ።
፴፬ እኔም ፡ እንደ ፡ ሥራቸው ፡ ክፋት ፡ መጠን ፡
ፍዳውን ፡ አመጣባቸዋለሁ ፡ አርሮ ፡ አመድ ፡
ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ሥጋቸውንም ፡ በእሳት ፡ አቃጥ
ላለሁ ፡ ነፋስ ፡ ይወስዳቸው ፡ ዘንድ ፡ በዚያም ፡
የሥጋቸውን ፡ አመድ ፡ እንደ ፡ ትቢያ ፡ በተራራ ፡
ላይ ፡ እበትናለሁ ፡ አለ ።
፴፭ ይኸንንም ፡ ከተናገረ ፡ በኋላ ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡
ቆይቶ ፡ እነዚያን ፡ የከበሩ ፡ ሰዎች ፡ ያመጧቸው ፡
ዘንድ ፡ አዘዘ ፡ እነዚያም ፡ የከበሩ ፡ ሰዎች ፡ በቀ
ረቡ ፡ ጊዜ ፡ በታላቁ ፡ ጉድጓድ ፡ ምድጃ ፡ ውስጥ ፡
እሳት ፡ ያነዱ ፡ ዘንድ ፡ እሳቱን ፡ የሚያናድድና ፡
ድስት ፡ የሚያፈሉበት ፡ የተንኮል ፡ ሥራን ፡
ስቡንና ፡ እንጆድን ፡ የባሕር ፡ አረፋና ፡ ሙጫን ፡
ድኙንም ፡ በውስጡ ፡ ይጨምሩ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ።
፴፮ በጉድጓዱም ፡ ያለ ፡ እሳት ፡ በነደደ ፡ ጊዜ ፡ መል
እክተኞቹ ፡ ያዘዝከንን ፡ አደረግን ፡ የሚጨመረ
ውን ፡ ሰው ፡ ስደድ ፡ ሲሉ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ሄዱ ።
፴፯ ተቀብለውም ፡ በእሳቱ ፡ ጉድጓድ ፡ ይጥሏቸው ፡
ዘንድ ፡ አዘዘ ፡ ብላቴኖቹም ፡ ንጉሡ ፡ እንዳዘዛ
ቸው ፡ አደረጉ ፡ እነዚያም ፡ የከበሩ ፡ ሰዎች ፡
ወደ ፡ እሳቱ ፡ በገቡ ፡ ጊዜ ፡ ነፍሳቸውን ፡ ለእግ
ዚአብሔር ፡ ሰጡ ።
፴፰ መላእክትም ፡ የጣሉዋቸው ፡ ሰዎች ፡ ሲያዩ ፡
ተቀብለው ፡ ነፍሳቸውን ፡ ይስሐቅና ፡ አብርሃም ፡
ያዕቆብ ፡ ወደ ፡ አሉበት ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ወደ
ሚገኝበት ፡ ወደ ፡ ገነት ፡ ወሰዷቸው ።

ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ ያም ፡ ወንጀለኛ ፡ እንደ ፡ ሞቱ ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡
አመድ ፡ እስኪሆን ፡ ድረስ ፡ ሥጋቸውን ፡ በእ
ሳት ፡ ያቃጥሉ ፡ ዘንድ ፡ በነፋስም ፡ ይበትኗ
ቸው ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፡ እሳቱ ፡ ግን ፡ ከሬሳቸው ፡
ወገን ፡ የሬሳውን ፡ ጠጉር ፡ ያቃጥል ፡ ዘንድ ፡
አልቻለውም ፡ ከጉድጓዱም ፡ አወጧቸው ።
፪ ዳግመኛም ፡ ከጧት ፡ ጀምረው ፡ እስከ ፡ ማታ ፡
ድረስ ፡ በላያቸው ፡ እሳት ፡ አነደዱ ፡ አላቃጠላ
ቸውም ፡ አሁንም ፡ ሬሳቸውን ፡ ኑ ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡
እንጣለው ፡ አሉ ።
፫ ንጉሡም ፡ እንዳዘዛቸው ፡ አደረጉ ፡ በባሕር ፡
ላይ ፡ ጣሏቸው ፡ ምንም ፡ ታላላቅ ፡ ደንጊያዎች
ንና ፡ የብረት ፡ ጉልቻዎችን ፡ አሀያ ፡ በመዘውር ፡
የሚፈጭበትን ፡ ወፍጮ ፡ ጨምረው ፡ ወደ ፡
ባሕር ፡ ቢጥሏቸው ፡ ባሕሩ ፡ ያሰጠማቸው ፡ ማስ
ጠም ፡ የለም ፡ የእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ ረድ
ኤት ፡ አድሮባቸዋልና ፡ በባሕሩ ፡ ላይ ፡ ዋኙ ፡
እንጂ ፡ አልሰጠሙም ፡ በተተነኮለባቸው ፡ ተን
ኮል ፡ ሁሉ ፡ እነሳቸውን ፡ ማጥፋት ፡ ተሳነው ።
፬ ከሕይወታቸውም ፡ ይህ ፡ ሞታቸው ፡ አድክሞ
ኛልና ፡ ይበሏቸው ፡ ዘንድ ፡ ሬሳቸውን ፡ ለአው
ሬዎች ፡ ልጣል ፡ እንጂ ፡ ምን ፡ አደርጋለሁ ፡ አለ ።
፭ ብላቴኖቹም ፡ እንዳዘዛቸው ፡ አደረጉ ፡ አሞሮ
ችና ፡ አውሬዎች ፡ ሬሳቸውን ፡ አልነኩትም ፡

ወሮችና ፡ አሞሮች ፡ በፀሐይ ፡ ከመቃጠል ፡ በክ
ንፋቸው ፡ ጋርደዋቸው ፡ ያምስቱ ፡ ሰማዕታት ፡
ሬሳቸው ፡ አሥራ ፡ አራት ፡ ቀን ፡ ተቀመጠ ።
፮፤ ባዩዋቸውም ፡ ጊዜ ፡ ሰውነታቸው ፡ እንደ ፡
ፀሐይ ፡ አበራ ፡ ብርሃን ፡ ድንኳኑን ፡ እንዲከብ ፡
መላእክትም ፡ ሬሳቸውን ፡ ከበቡት ።
፯፤ ምክርን ፡ መከረ ፡ የሚያደርገውን ፡ አጣ ፡ ከዚ
ህም ፡ በኋላ ፡ መቃብር ፡ ቆፍሮ ፡ ያምስቱን ፡
ሰማዕታት ፡ ሬሳቸውን ፡ ቀበረ ።
፰፤ ያንንም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ የዘነጋ ፡ ንጉሥ ፡
ሌሊት ፡ ባልጋ ፡ ተኝቶ ፡ ሳለ ፡ አምስቱ ፡ ሰማዕ
ታት ፡ ተቆጥተው ፡ ሰይፋቸውን ፡ ይዘው ፡
ሌሊት ፡ በሬቱ ፡ ቁመው ፡ ታዩት ።
፱፤ ሌሊት ፡ በወንጀል ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ የገቡ ፡ መስሎ
ታልና ፡ ከእንቅልፉ ፡ በነቃ ፡ ጊዜ ፡ ፈርቶ ፡ ከአ
ልጋው ፡ ወደ ፡ አዳራሹ ፡ ይሸሽ ፡ ዘንድ ፡ ወደደ ፡
የወንጀሉትም ፡ መሰለው ፡ የሚገድሉት ፡ መስ
ሎታልና ፡ ፈርቶ ፡ ጉልበቱ ፡ ተንቀጠቀጠ ።
፲፤ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ጌቶቼ ፡ ምን ፡ ትወዳላችሁ ፡
እኔስ ፡ ምን ፡ ላድርግላችሁ ፡ አለ ።
፲፩፤ በእሳት ፡ አቃጥለህ ፡ የገደልከን ፡ እኛንም ፡ በባ
ሕር ፡ ላይ ፡ ይጥሉ ፡ ዘንድ ፡ ያዘዝህ ፡ እኛ ፡ አይ
ደለምን ፡ ብለው ፡ መለሱለት ፡ ስላመንበት ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ሰውነታችንን ፡ ጠብቆናልና ፡ እኛን ፡
ማጥፋት ፡ ተሳነህ ፡ በሱ ፡ ያመነ ፡ ሰው ፡ አይጠፋ
ምና ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ክብር ፡ ምስጋና ፡ ይግ
ባውና ፡ ያመንበት ፡ እኛም ፡ በመከራው ፡ አላ
ፈርንም ።
፲፪፤ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ቅጣት ፡ እንዲያገኝኝ ፡ አላወቅ
ሁምና ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡ ስላደረግሁብችሁ ፡ ፈንታ ፡
ምን ፡ ዋጋ ፡ ልስጣችሁ ።
፲፫፤ ሰውነቴን ፡ በሞት ፡ እንዳትወስዱ ፡ በሕይወት ፡
ሳለሁ ፡ ወደ ፡ ሲኦልም ፡ እንዳታወርዱኝ ፡ እሁ
ንም ፡ የምሰጣችሁን ፡ ዋጋ ፡ ለዩልኝ ።
፲፬፤ እኔ ፡ በድያችኋለሁና ፡ ያበታችሁ ፡ የእግዚአብ
ሔር ፡ ሕግ ፡ ርኅራኄ ፡ ስለሆነ ፡ ኃጢአቴን ፡
ይቅር ፡ በሉኝ ፡ አላቸው ።
፲፭፤ እነዚያም ፡ የከበሩ ፡ ሰማዕታት ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡
ስላደረግህብን ፡ ፈንታ ፡ እኛስ ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡
አንከፍልህም ፡ በነፍስ ፡ ፍዳ ፡ የሚያመጣ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ነውና ፡ ፍዳንስ ፡ የሚከፍልህ ፡ ፈጣ
ሪያችን ፡ እግዚአብሔር ፡ አለ ።
፲፮፤ ነገር ፡ ግን ፡ ለውቀትህ ፡ ማነስና ፡ ስለ ፡ ልቡ
ናህ ፡ ድንቁርና ፡ እኛ ፡ ደጎኖች ፡ እንደሆንን ፡
ተገልጦን ፡ ታየንህ ፡ እኛንስ ፡ የገደልከን ፡ መስ
ሎህ ፡ ደኅንነትን ፡ አዘጋጀህልን ።
፲፯፤ የጣዖቶችህ ፡ ካህናትና ፡ አንተ ፡ ግን ፡ ለዘለዓ
ለሙ ፡ መውጫ ፡ ወደ ፡ ሌለበት ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡
ትወዳርላችሁ ።
፲፰፤ ለምታመልኳቸው ፡ እንደ ፡ ምራቅ ፡ የተናቃ
ችሁ ፡ ስትሆኑ ፡ ለፈጠራችሁ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
መስገድ ፡ ትታችሁ ፡ ለምትሰግዱላቸው ፡ ለጣዖ
ቶችህና ፡ ለናንተ ፡ ወዮላችሁ ፡ ካለመኖር ፡ ወደ ፡
መኖር ፡ አምጥቶ ፡ የፈጠራችሁ ፡ እግዚአብሔ
ርንም ፡ አታውቁም ፡ ዛሬ ፡ እንደ ፡ ጢስ ፡ ታይ
ታችሁ ፡ ነገ ፡ የምትጠፉ ፡ አይደላችሁምን ፡
ብለው ፡ መለሱለት ።
ንጉሡም ፡ የወደዳችሁትን ፡ ሁሉ ፡ አደርግላ ፲፱፤
ችሁ ፡ ዘንድ ፡ ምን ፡ ታገዙኛላችሁ ፡ ብሎ ፡
መለሰላቸው ።
ወደ ፡ ገሃነመ ፡ እሳት ፡ እንዳትገባ ፡ ራስህን ፡ ፳፤
ለማዳን ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የምናስተምርህ ፡ ራሳች
ንን ፡ ለማዳን ፡ አይደለም ።
ጣዖቶቻችሁ ፡ ልቡናና ፡ ነፍስ ፡ ዕውቀት ፡ የሌ ፳፩፤
ላቸው ፡ የሰው ፡ እጅ ፡ የሠራቸው ፡ ብርና ፡
ወርቅ ፡ ደንጊያና ፡ እንጨት ፡ ናቸውና ።
እነርሳቸው ፡ ግን ፡ አይገድሉም ፡ አያድኑም ፡ ፳፪፤
ወዳጃቸውን ፡ አይጠቅሙም ፡ ጠላታቸውን ፡
አይጎዱም ፡ አያዋርዱም ፡ አያከብሩም ፡ ባለ
ጸጋ ፡ አያደርጉም ፡ አያደኸዩም ፡ ከሰው ፡ አንዱ ፡
ይድን ፡ ዘንድ ፡ በማይወዱ ፡ በአጋንንት ፡ ሥል
ጣን ፡ እናንተን ፡ ያስታሉ ፡ እንጂ ፡ አይነቅሉም ፡
አይተክሉም ።
እናንተ ፡ የሠራችኋቸው ፡ ስትሆኑ ፡ እነርሳቸው ፡ ፳፫፤
የፈጠሩዋችሁ ፡ የሚመስሏችሁ ፡ እናንተ ፡ ልበ ፡
ደንቆሮዎች ፡ ይልቁንም ፡ እንደናንተ ፡ ያሉት ፡
ሰዎች ፡ ከሞት ፡ ይድኑ ፡ ዘንድ ፡ አይወዱም ።
የሰይጣናትና ፡ የአጋንንት ፡ ሥልጣን ፡ አድሮባ ፳፬፤
ቸዋልና ፡ በባሕረ ፡ ገሃነም ፡ ውስጥ ፡ ያሰጥማ
ችሁ ፡ ዘንድ ፡ እንደወደዳችሁ ፡ ነገርን ፡ ይመል
ሱላችኋል ።
አንተ ፡ ግን ፡ ይኸንን ፡ ስሕተትህን ፡ ትተህ ፡ ፳፭፤
ፈጣሪያችን ፡ እግዚአብሔርን ፡ አምልከው ፡
ነፍሳችንን ፡ እንጠቀማት ፡ ዘንድ ፡ ይኸም ፡ ስለ
ሞትን ፡ ፈንታ ፡ ዋጋችን ፡ ይሁን ፡ አሉት ።
እርሱ ፡ ግን ፡ ደንግጦ ፡ ፈጽሞ ፡ ያደንቅ ፡ ነበር ፡ ፳፮፤
አምስቱም ፡ ሁሉ ፡ ሰይፋቸውን ፡ መዝዘው ፡
ታይተውታልና ፡ ፈራ ፡ ስለዚህም ፡ ነገር ፡ ሰገ
ደላቸው ።
እንግዲህስ ፡ ትቢያ ፡ የሆኑ ፡ ሙታን ፡ ከሞቱ ፡ ፳፯፤
በኋላ ፡ በውነት ፡ እንዲነሡ ፡ አወቅሁ ፡ እኔስ ፡
ልሞት ፡ ጥቂት ፡ ብቻ ፡ ቀርቶኝ ፡ ነበር ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ከዚያ ፡ ከንጉሡ ፡ ፊት ፡ ተሠ ፳፰፤
ወሩ ፡ ከዚያች ፡ ቀን ፡ ወዲያ ፡ ፈጽሞ ፡ ትዕቢ
ተኛ ፡ የሚሆን ፡ ያ ፡ ጺሩጻይዳን ፡ ሬሳቸውን ፡
ማቃጠል ፡ ተወ ።
ብዙ ፡ ዘመን ፡ አስተውታልና ፡ በጣዖቶቹና ፡ ፳፱፤
በልቡናው ፡ ስሕተት ፡ ደስ ፡ ይለው ፡ ነበር ፡ የፈ
ጠራቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ በአምልኮ ፡ መከ
ተል ፡ እስኪተዉ ፡ ድረስ ፡ እንደርሱ ፡ ያሉ ፡
ብዙ ፡ ሰዎችንም ፡ አሳተ ፡ እንጂ ፡ እርሱ ፡ ብቻ ፡
የሳተ ፡ አይደለም ።
ሴቶች ፡ ልጆቻቸውንና ፡ ወንዶች ፡ ልጆቻቸው ፴፤
ንም ፡ ለአጋንንት ፡ ይሠዉ ፡ ነበር ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ የማይወደው ፡ መዳራትን ፡ ሁከትን ፡ ያደ
ርግ ፡ ዘንድ ፡ አበታቸው ፡ ሰይጣን ፡ ያስተማራ
ቸው ፡ የልቡናቸው ፡ ፈቃድ ፡ የሚሆን ፡ መዳ
ራትና ፡ ሁከትን ፡ ይሠራሉ ፡ እንጂ ።

፴፭፤ እናታቸውን ፡ ያገቡሉ ፡ አክስቶቻቸውንና ፡ እቶ
ቻቸውንም ፡ ያጎሰቍሉሉ ፡ ይህንን ፡ ያደረ ፡
ሥራ ፡ የሚመስለውን ፡ ሁሉ ፡ እየሠሩ ፡ ሰውነ
ታቸውን ፡ ያጎስቍላሉ ፡ ሰይጣን ፡ የነዚያን ፡
ጠማሞች ፡ ሰዎች ፡ ልቡናቸውን ፡ አጥንቶታ
ልና ፡ እንመለስም ፡ አሉ ፡፡
፴፮፤ ፈጣሪውን ፡ የማያውቅ ፡ ያ ፡ ጺሩጻይዳን ፡ ግን ፡
ፈጽሞ ፡ ትዕቢተኛ ፡ ነበር ፡ በጣዖቶቹም ፡
ይመካ ፡ ነበር ፡፡
፴፯፤ እግዚአብሔር ፡ በሕግ ፡ በአምልኮ ፡ ለማያው
ቁት ፡ ሰዎች ፡ መንግሥትን ፡ እንዴት ፡ ይሰ
ጣል ፡ ቢሉ ፡ በንስሐ ፡ ፈጽመው ፡ ወደርሱ ፡
ይመለሱ ፡ እንደሁ ፡ ይፈትናቸዋልና ፡ ስለዚህ ፡
ነው ፡፡
፴፰፤ እነሱ ፡ ግን ፡ ፈጽመው ፡ በንስሐ ፡ ቢመለሱ ፡
ይወዳቸው ፡ ነበር ፡ መንግሥታቸውንም ፡ ይጠ
ብቅ ፡ ነበር ፡ እምቢ ፡ ቢሉ ፡ ግን ፡ ለዘለዓለሙ ፡
በእሳት ፡ ገሃነም ፡ እሳት ፡ ይቀጣቸዋል ፡፡
፴፱፤ ንጉሥ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ጌትነቱ ፡ ገናናነት ፡ ፈጣ
ሪው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ሊፈራው ፡ ይገባው ፡
ነበር ፡ ዳኛም ፡ እንደ ፡ ግዛቱ ፡ ገናንነት ፡ በጎ ፡
ፍርድ ፡ እየፈረደ ፡ ለፈጣሪው ፡ ሊገዛ ፡ ይገባ ፡
ነበር ፡፡
፵፤ ሽማግሎችና ፡ አለቆችም ፡ ራቅ ፡ ማሠሪያዎ
ችንና ፡ ጥቃቅን ፡ ነገሥታትም ፡ እንደ ፡ ጌትነታ
ቸው ፡ ብዛት ፡ መጠን ፡ ለፈጣሪያቸው ፡ ሊታዘዙ ፡
ይገባ ፡ ነበር ፡፡
፵፩፤ ፍጥረቱን ፡ ሁሉ ፡ የፈጠረ ፡ የሰማይና ፡ የምድር ፡
ጌታ ፡ እሱ ፡ ነውና ፡ የሚያደኸይ ፡ ባለጸጋ ፡ የሚ
ያደርግ ፡ በምድርና ፡ በሰማይ ፡ ሌላ ፡ ፈጣሬ ፡
ስለሌለ ፡ የሚያከብርና ፡ የሚያዋርድ ፡ እሱ ፡
ነው ፡፡

ምዕራፍ ፡ ፯ ፡፡

፩፤ ከሰሳው ፡ አርበኞች ፡ አንዱ ፡ አርበኛ ፡ ከሩ ፡
በንዲት ፡ ማንክ ፡ ድኝ ፡ ከእግሩ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡
ራሱ ፡ ድረስ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሰውነቱ ፡ እንዲ
ያብጥ ፡ አደረገው ፡ በንዲት ፡ ፌሬ ፡ ሞተ ፡፡
፪፤ ዳግመኛም ፡ ከኃይለኛነቱ ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ የብ
ረት ፡ አልጋ ፡ ያሠራ ፡ ኪራም ፡ ከሩ ፡ እሱንም ፡
እግዚአብሔር ፡ በሞት ፡ ሸሸገው ፡፡
፫፤ ዳግመኛም ፡ ናቡከደነፆር ፡ ያለኔ ፡ ሌላ ፡ ንጉሥ ፡
የለም ፡ በዚህ ፡ ዓለምም ፡ ፀሐይን ፡ የማወጣ ፡
ፈጣሪ ፡ እኔ ፡ ነኝ ፡ ብሎ ፡ ከሩ ፡ ከትዕቢቱም ፡
ብዛት ፡ የተነሣ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡፡
፬፤ እግዚአብሔርም ፡ ከሰው ፡ ለይቶ ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡
ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሰደደው ፡ የፈጠረው ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እስኪያውቅ ፡ ድረስ ፡
ዕድሉንም ፡ ከሰማይ ፡ ወፎችና ፡ ከምድረ ፡ በዳ ፡
አውሬዎች ፡ ጋራ ፡ አደረገው ፡፡
፭፤ በአምልኮ ፡ በወቀውም ፡ ጊዜ ፡ ዳግመኛ ፡ ወደ ፡
መንግሥቱ ፡ መለሰው ፡ ተደፋፍሮ ፡ በፈጠረው ፡
በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ ክርቶ ፡ መሬት ፡ ያልሆነ ፡
ማነው ፡፡

ሕጉን ፡ ሥርዓቱንስ ፡ አፍርሰ ፡ መሬት ፡ ያልዋ ፮፤
ጠችው ፡ ማነው ፡፡
ጺሩጻይዳን ፡ አንተም ፡ በፈጣሪህ ፡ ላይ ፡ ትከራ ፡ ፯፤
ዘንድ ፡ ተወዳለህ ፡ አንተም ፡ ዳግመኛ ፡ ከትዕ
ቢትህ ፡ የተነሣ ፡ እንደ ፡ እነሱቸው ፡ ያጠፋህ ፡
ዘንድ ፡ ወደ ፡ መቃብርም ፡ ያወርድህ ፡ ዘንድ ፡
አለህ ፡፡
ዳግመኛም ፡ ጥርስ ፡ ማፋጨትና ፡ ልቅሶ ፡ ወዳ ፰፤
ለበት ፡ የጨለማ ፡ ፍጻሜ ፡ ወደ ፡ ሆነ ፡ ወደ ፡
ሲኦል ፡ ከገቡም ፡ በኋላ ፡ ለዘለዓለሙ ፡ መውጫ ፡
ወደሌለበት ፡ ወደ ፡ ጥልቅ ፡ ጕድጓድ ፡ ወደ ፡
ገሃነም ፡ ያወርድህ ፡ ዘንድ ፡ አለህ ፡፡
አንተስ ፡ እንዳንተ ፡ እንደ ፡ ነበሩ ፡ የዚህን ፡ ፱፤
ዓለም ፡ ኑሮ ፡ እንደ ፡ ተወ ፡ እንደ ፡ ትዕቢተኞች ፡
ነገሥታት ፡ ነግ ፡ የምትሞት ፡ የምትፈርስ ፡ ሰው ፡
ነህ ፡፡
እኛስ ፡ አንተ ፡ ፈራሽ ፡ በስባሽ ፡ ነህ ፡ እግዚአ ፲፤
ብሔር ፡ ግን ፡ ምድርና ፡ ሰማይን ፡ አንተንም ፡
የፈጠረ ፡ ነውና ፡ እግዚአብሔር ፡ አይደለህም ፡
እንላለን ፡፡
እርሱ ፡ ትዕቢተኞችን ፡ ያዋርዳቸዋል ፡ የተዋረ ፲፩፤
ዱትን ፡ ያከብራቸዋል ፡ እርሱ ፡ ለደከሙ ፡ ሰዎች ፡
ጽናትን ፡ ይሰጣቸዋል ፡፡
እርሱ ፡ ደጎኖችን ፡ ይገድላል ፡ እርሱ ፡ በመቃ ፲፪፤
ብር ፡ ተቀብረው ፡ መሬት ፡ የሆኑትን ፡ የሞቱ
ትን ፡ ሰዎች ፡ ያስነሣቸዋል ፡፡
በሮችንም ፡ ከኃጢአት ፡ አገዛዝ ፡ በሕይወት ፡ ፲፫፤
ነፃ ፡ ያወጣቸዋል ፡፡
ጺሩጻይዳን ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ፡ ጥቅም ፡ በሌላቸው ፡ ፲፬፤
በረከሱ ፡ ጣዖቶችህ ፡ ለምን ፡ ትመካለህ ፡፡
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ምድርና ፡ ሰማይን ፡ ታላ ፲፭፤
ላቅ ፡ ባሕርንም ፡ ፈጠረ ፡ ጨረቃና ፡ ፀሐይን ፡
ፈጠረ ፡ ዘመኖችንም ፡ አዘጋጀ ፡፡
ሰው ፡ ወደ ፡ እርሻው ፡ ይሰማራል ፡ እስኪመ ፲፮፤
ሽም ፡ ድረስ ፡ ሲያርስ ፡ ይውላል ፡ የሰማይ ፡
ከዋክብትም ፡ በቃሉ ፡ ጸንተው ፡ ይኖራሉ ፡፡
ሁሉንም ፡ በሰማይ ፡ ይጠራቸዋል ፡ እግዚአብ ፲፯፤
ሔር ፡ ሳያውቀው ፡ የሚደረግ ፡ ነገር ፡ የለም ፡፡
ያገለግሉት ፡ ዘንድ ፡ የከበረ ፡ ስሙንም ፡ ያመሰ ፲፰፤
ግኑ ፡ ዘንድ ፡ የሰማይ ፡ መላእክትን ፡ እርሱ ፡
አዘዘ ፡ መላእክትም ፡ ሕይወትን ፡ ወደሚወርሱ ፡
ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ይላካሉ ፡፡
አገልጋይ ፡ የሆነ ፡ ሩፋኤል ፡ ወደ ፡ ጦቢት ፡ ተላከ ፡ ፲፱፤
ጦብያንም ፡ በራጉኤል ፡ አገር ፡ ከሞት ፡ አዳ
ነው ፡፡
ቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡ የኢሎፍሊን ፡ ሰዎች ፡ በሚ ፳፤
ያጠፋቸው ፡ ገንዘብ ፡ ልብ ፡ ያስደርገው ፡ ዘንድ ፡
ወደ ፡ ጌዴዎን ፡ ተላከ ፤ እስራኤልንም ፡ የኤር
ትራን ፡ ባሕር ፡ ባሻገራቸው ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ነቢዩ ፡
ወደ ፡ ሙሴ ፡ ተላከ ፡፡
እግዚአብሔር ፡ ብቻ ፡ መራቸው ፡ ብዒልና ፡ ከን ፳፩፤
ርሰቸው ፡ ጋራ ፡ ልዩ ፡ ጣዖት ፡ አልነበረም ፡፡
በምድር ፡ ላይ ፡ ወዳለ ፡ አገመራም ፡ አወጣቸው ፡፡ ፳፪፤
የኩዳዱንም ፡ እህል ፡ መገቢቸው ፡ ፈጽሞ ፡ ወደ ፳፫፤

ቸዋልና ፡ እንደ ፡ ደንጊያ ፡ የጸናውን ፡ ማር ፡
መግበ ፡ ተከባከባቸው ።
፳፬ እንተም ፡ ወገኖቹን ፡ በሚገበ ፡ ፈጽመህ ፡
ትጠብቅ ፡ ዘንድ ፡ የፈጠረህ ፡ የእግዚአብሔር
ንም ፡ ፈቃዱን ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ፡ በራቱ ፡ መን
ግሥት ፡ ላይ ፡ ሥልጣን ፡ ሰጥቶ ፡ አነገሠህ ።
፳፭ ከሁሉ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አድርጎ ፡ አንግሦሃልና ፡ ፈጣ
ሪህ ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ትወደው ፡ ዘንድ ፡
ፈጽሞ ፡ አነገሠህ ።
፳፮ እንደወደደህ ፡ በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ ሁሉ ፡ እንዳመ
ነህ ፡ አንተም ፡ ፈጣሪህ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፈጽ
መህ ፡ ትወደው ፡ ዘንድ ፡ አገባብ ፡ ነው ፡ በዚህ ፡
ዓለም ፡ ዘመንህ ፡ ይበዛ ፡ ዘንድ ፡ ካንተም ፡ ጋራ ፡
በረድኤት ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡ አንተም ፡ የእግዚአ
ብሔር ፡ ፈቃዱን ፡ አድርግ ።
፳፯ በጠላቶችህም ፡ ላይ ፡ ጠበቃ ፡ ሆኖ ፡ ይቆምልህ ፡
ዘንድ ፡ በዘሩንህም ፡ ያስቀምጥህ ፡ ዘንድ ፡ ራስ
ህንም ፡ በክንፈ ፡ ረድኤቱ ፡ ይሠውርህ ፡ ዘንድ ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ፈቃድ ፡ አድርግ ።
፳፰ ባታውቅስ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሳኦልን ፡ ከእስራ
ኤል ፡ ልጆች ፡ መርጦ ፡ ያባቱን ፡ አህዮች ፡ ሲጠ
ብቅ ፡ በወገኖቹ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ እንዳነገ
ሠው ፡ አንተንም ፡ መርጦ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡
አነገሠህ ፡ እሱም ፡ ከእስራኤል ፡ ጋራ ፡ በዙፋኑ ፡
ላይ ፡ ተቀመጠ ።
፳፱ ከወንድሞቹ ፡ ለይቶ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ዕድልንም ፡
ሰጠው ፡ እግዚአብሔር ፡ በወገኖቹ ፡ ላይ ፡ አነገ
ሠህ ፡ እንግዴህ ፡ ወዲህስ ፡ እነሆ ፡ ወገኖቹን ፡
ጠብቅ ።
፴ ትገድል ፡ ዘንድ ፡ ታድንም ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ በላያቸው ፡ ሾሞሃልና ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ የሚ
ሠሩትን ፡ በበጎ ፡ ነገር ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ የሚሠሩት
ንም ፡ በክፉ ፡ ነገር ፡ ጠብቃቸው ፡ አለው ።
፴፩ እየገረፍክም ፡ እያዳንክም ፡ ቢሆን ፡ ፈቃዱን ፡
ታደርግ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ አንተን ፡
በሁሉ ፡ ላይ ፡ ሾሞሃልና ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ የሚሠ
ሩትን ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ የሚሠሩትን ፡
ክፉ ፡ ሥራ ፡ ክፈላቸው ።
፴፪ አንተ ፡ በሰማይ ፡ ያለ ፡ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ የእግ
ዚአብሔር ፡ ባሪያ ፡ ነህና ፡ በስብከው ፡ ሁሉ ፡
በፊቱ ፡ እየተለማመጥህ ፡ በለመንከውም ፡ ሁሉ ፡
ፈቃድህን ፡ ያደርግልህ ፡ ዘንድ ፡ አንተም ፡ የእ
ግዚአብሔርን ፡ ፈቃድ ፡ አድርግ ።
፴፫ እሱን ፡ የሚገዛው ፡ የለም ፡ እሱ ፡ ግን ፡ ሁሉን ፡
ይገዛል ።
፴፬ እሱን ፡ የሚሾመው ፡ የለም ፡ እሱ ፡ ግን ፡ ሁሉን ፡
ይሾማል ።
፴፭ እሱን ፡ የሚሽረው ፡ የለም ፡ እሱ ፡ ግን ፡ ሁሉን ፡
ይሽራል ።
፴፮ እሱን ፡ የሚነቅፈው ፡ የለም ፡ እሱ ፡ ግን ፡ ሁሉን ፡
ይነቅፋል ።
፴፯ እሱን ፡ የሚያተጋው ፡ የለም ፡ እሱ ፡ ግን ፡ ሁሉን ፡
ያተጋል ፡ የሰማይና ፡ የምድር ፡ አገዛዝ ፡ የሱ ፡
ነውና ፡ ከሥልጣኑ ፡ የሚያመልጥ ፡ የለም ፤ በሱ ፡
ዘንድ ፡ ሁሉ ፡ የተገለጠ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ከፊቱ ፡
የተሠወረ ፡ የለም ።
፴፰ ሁሉን ፡ ያያል ፡ እሱን ፡ ግን ፡ የሚያየው ፡ የለም ፡
ወደሱ ፡ አድነኝ ፡ ብሎ ፡ የሚጸልየውን ፡ ሰው ፡
ጸሎቱን ፡ ይሰማዋል ፡ ሰውን ፡ በሱ ፡ አምሳል ፡
ፈጥሮታልና ፡ ልመናውንም ፡ ይቀበለዋል ።
፴፱ እስከ ፡ ዘለዓለሙ ፡ የሚኖር ፡ ንጉሥ ፡ ነውና ፡
ከማይለወጥ ፡ ባሕርዩ ፡ ሁሉን ፡ ይመግባል ።

ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩ ፈቃዱን ፡ የሚያደርጉ ፡ ነገሥታቱን ፡ በው
ነት ፡ ያነግሣቸዋልና ፡ ነገሥታቱ ፡ ስለሱ ፡ የቀና ፡
ነገርን ፡ ጻፉ ።
፪ የእግዚአብሔርን ፡ ፈቃድ ፡ አድርገዋልና ፡ ይስ
ሐቅና ፡ አብርሃም ፡ ያዕቆብም ፡ ሰሎሞንና ፡
ዳዊት ፡ ሕዝቅያስም ፡ ማደሪያቸው ፡ ብርሃን ፡
የሆነች ፡ ያማሩ ፡ ነገሥታት ፡ ሁሉ ፡ በሉበት ፡
በገነት ፡ ማደሪያቸውን ፡ በማይመረመር ፡ ብር
ሃን ፡ ያበራል ።
፫ የሰማይ ፡ አዳራሽ ፡ ፈጽሞ ፡ የበራ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡
የምድር ፡ አዳራሽ ፡ እንደ ፡ ሰማይ ፡ አዳራሽ ፡
አይደለም ፡ መልኩ ፡ የብርና ፡ የወርቅ ፡ የዕን
ቍም ፡ መልክ ፡ የሚሆን ፡ ወልወሉ ፡ ንጹሕ ፡
ነው ።
፬ ፈጽሞ ፡ የሚያበራ ፡ መልኩም ፡ በሰው ፡ ልቡና ፡
የማይመረመር ፡ ነው ፡ የሰማይ ፡ አዳራሽ ፡ እንደ ፡
ዕንቍ ፡ የሚያበራ ፡ ነው ።
፭ የባሕርይ ፡ አዋቂ ፡ የሆነ ፡ እግዚአብሔር ፡ እርሱ ፡
እንዳወቀ ፡ የፈጠረው ፡ የሰማይ ፡ አዳራሽ ፡
የሰው ፡ ልቡና ፡ የማይመረምረው ፡ በፍጹም ፡
ብርሃን ፡ የሚያበራ ፡ ነው ፡ በብርና ፡ በወርቅ ፡
በዕንቍ ፡ በንጭ ፡ ሐርና ፡ በሰማያዊ ፡ ሐርም ፡
የተሠራ ፡ ወልወሉ ፡ ንጹሕ ፡ ነው ።
፮ እንደዚህ ፡ እጅግ ፡ ፈጽሞ ፡ ያማረ ፡ ነው ።
፯ በሃይማኖትና ፡ በምግባር ፡ የጸኑ ፡ ጻድቃን ፡
በእግዚአብሔር ፡ ቸርነትና ፡ ለይቅርታ ፡ የሚወ
ርሱት ፡ ነው ።
፰ ከርሱም ፡ የሚፈስ ፡ የደግነት ፡ ውኃ ፡ አለ ፡
ፈጽሞም ፡ እንደ ፡ ፀሐይ ፡ ያበራል ፡ በውስ
ጡም ፡ የብርሃን ፡ ድንኳን ፡ አለ ፡ በጸጋ ፡ ሽቱም ፡
የተከበበ ፡ ነው ።
፱ ያማረ ፡ የተወደደ ፡ የሆነ ፡ መልኩ ፡ ጣዕሙ ፡
ልዩ ፡ የሆነ ፡ የገነት ፡ ፍሬም ፡ በቤቱ ፡ ዙሪያ ፡
አለ ፡ በዚያም ፡ የዘይትና ፡ የወይን ፡ ቦታ ፡ አለ ፡
ፈጽሞም ፡ ያማረ ፡ ነው ፡ የፍሬውም ፡ መዓዛ ፡
የጣፈጠ ፡ ነው ።
፲ ሥጋዊ ፡ ደማዊ ፡ ሰው ፡ ወደሱ ፡ ሲገባ ፡ ከመዓ
ዛው ፡ ጣዕም ፡ የተነሣ ፡ በርሱ ፡ ካለተድላ ፡ ደስታ ፡
ብዛት ፡ ነፍሱ ፡ ከሥጋው ፡ በተለየች ፡ ነበር ።
፲፩ የእግዚአብሔርን ፡ ፈቃድ ፡ ያደረጉ ፡ ያማሩ ፡
ነገሥታት ፡ በዚያ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፡ ክብራቸ
ውና ፡ በታቸው ፡ ድኅነት ፡ በሚገኝበት ፡ ዘለዓ
ለም ፡ ጸንቶ ፡ በሚኖር ፡ በመንግሥት ፡ ሰማይ ፡
የታወቀ ፡ ነው ።

፲፪፡ በምድር ፡ ያለ ፡ ጌትነታቸው ፡ የገነነ ፡ የከበረ ፡
እንደ ፡ ሆነ ፡ በሰማይ ፡ ያለ ፡ ጌትነታቸውም ፡
የገነነ ፡ የከበረ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አሳየ ፤ በዚህ ፡
ዓለም ፡ እንዲያከብሯቸው ፡ እንዲሰግዱላቸው ፡
በሰማይ ፡ ይከብራሉ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላሉ ፡
በዚህ ፡ ዓለም ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ ቢሠሩ ፡ ደስ ፡ ይላ
ቸዋል ።
፲፫፡ እግዚአብሔር ፡ በሰጣቸው ፡ ግዛታቸውና ፡ መን
ግሥታቸው ፡ ክፉ ፡ የሆኑ ፡ ነገሥታት ፡ ግን ፡
በውነት ፡ በሚገባ ፡ አይፈርዱም ፡ የጦም ፡ አዳ
ሪዎችና ፡ የድኆችን ፡ ጩኸት ፡ ቸል ፡ ብለዋ
ልና ፡ ስደተኞውንና ፡ የተበደለውን ፡ አባት ፡
እናት ፡ የሞቱበትን ፡ ልጅ ፡ እውነት ፡ ፈርደው ፡
አያድኑም ።
፲፬፡ ጦም ፡ አዳሪዎችና ፡ ድኆችን ፡ ከሚቀማቸው ፡
ከባለጸጋው ፡ እጅ ፡ አያድኗቸውም ፡ ከምግባ
ቸው ፡ ከፍለው ፡ ሰጥተው ፡ የተራቡትን ፡ አያ
ጠግቧቸውም ፡ ከመጠጣቸውም ፡ ከፍለው ፡
ሰጥተው ፡ የተጠሙትን ፡ ሰዎች ፡ አያጠጧቸ
ውም ፡ ጆሯቸውንም ፡ ወደ ፡ ድኃው ፡ ጩኸት ፡
አልመለሱም ።
፲፭፡ እነርሳቸውንም ፡ የጨለማ ፡ መጨረሻ ፡ ወደ ፡
ሆነ ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡ ይወስዷቸዋል ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ የሚመጣበት ፡ ያች ፡ ከፍ ፡ ያለች ፡ ቀን ፡
በደረሰችባቸው ፡ ጊዜ ፡ ዳዊት ፡ በምስጋናው ፡
አቤቱ ፡ በፍርድህ ፡ አትቅሠፈኝ ፡ በመቅሠፍ
ትህም ፡ አትገሥፀኝ ፡ ብሎ ፡ እንደተናገረ ፡ መዓ
ቱም ፡ በተደረገባቸው ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ገናንነታ
ቸው ፡ ብዛት ፡ መጠን ፡ ችጋራቸውና ፡ ውርደ
ታቸው ፡ ይበዛል ።
፲፮፡ መኳንንትና ፡ ነገሥታት ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ይህን ፡
ዓለም ፡ የሚገዙ ፡ ሲሆኑ ፡ ሕግህን ፡ ያልጠበቁ ፡
ሰዎች ፡ አሉ ።
፲፯፡ በሰማይ ፡ ግን ፡ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ እግዚአብሔር ፡
አለ ፡ የሰው ፡ ሁሉ ፡ ነፍስ ፡ የሰውም ፡ ሁሉ ፡
ድኅነት ፡ በሥልጣኑ ፡ ተይዟል ፡ ለሚያከብሩት ፡
ሰዎች ፡ ክብርን ፡ የሚሰጣቸው ፡ እሱ ፡ ነው ፡
ፈጽሞ ፡ ሁሉን ፡ ይገዛልና ፡ የሚወዱትንም ፡
ሰዎች ፡ ይወዳቸዋል ።
፲፰፡ እሱ ፡ የምድርና ፡ የሰማይ ፡ ጌታ ፡ ነውና ፡ ኰላ
ሊት ፡ ያመላለሰውን ፡ ልቡና ፡ ያሰበውን ፡ መር
ምሮ ፡ ያውቃል ፡ ወደሱም ፡ በንጹሕ ፡ ልቡና ፡
ለለመነ ፡ ሰው ፡ የልመናውን ፡ ዋጋውን ፡ ይሰ
ጠዋል ።
፲፱፡ እናት ፡ አባቱ ፡ በሞቱበት ፡ ልጁና ፡ በባልቴ
ቶች ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ የሚሠሩ ፡ የኃይለኞች ፡ ትዕ
ቢትን ፡ ያጠፋል ።
፳፡ ይህን ፡ መንግሥት ፡ የያዝከው ፡ በኃይልህ ፡ አይ
ደለም ፡ ከዚህ ፡ ዙፋን ፡ ላይ ፡ የተቀመጥህ ፡ በመ
ቻልህ ፡ አይደለም ፡ በዚያ ፡ ወራት ፡ ወገኖቼን ፡
እንደ ፡ ገዛ ፡ እንደ ፡ ሳኦል ፡ መግዛት ፡ ይቻልህ ፡
እንደሁ ፡ ሊፈትንህ ፡ እርሱ ፡ ወዶ ፡ በመንግ
ሥት ፡ ዙፋን ፡ ላይ ፡ አስቀመጠህ ፡ እንጂ ፡
ይኸን ፡ መንግሥት ፡ የያዝኸው ፡ በኃይልህ ፡
አይደለም ፡ የነቢዩ ፡ የሳሙኤልን ፡ ቃልና ፡ የእ
ግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ቸል ፡ ብሎ ፡ ሠራዊቱ
ንና ፡ የማሌቅን ፡ ንጉሥ ፡ እንዳልገደለ ፡ እንደ ፡
ሳኦል ፡ ሲፈትንህ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ይህን ፡ መንግ
ሥት ፡ የያዝኸው ፡ በመቻልህ ፡ አይደለም ።
እግዚአብሔርም ፡ ነቢዩ ፡ ሳሙኤልን ፡ ሒደህ ፡ ፳፩፡
ሕግ ፡ በማፍረስ ፡ ጣዖቶቹንም ፡ በማምለክ ፡
ለጣዖቱም ፡ በመስገድ ፡ በመስጊዳቸውም ፡
ጥቅም ፡ በሌለው ፡ በተጠላ ፡ ሥራቸውም ፡ ሁሉ ፡
አሳዝነውኛልና ፡ ሳኦልን ፡ ወደ ፡ አማሌቅ ፡ አገር ፡
ሒደህ ፡ ከሰው ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ከብት ፡ ድረስ ፡
ሠራዊቶቻቸውንና ፡ ነገሥታቱን ፡ ሁሉ ፡ አጥፋ ፡
በለው ፡ አለው ።
እግዚአብሔርን ፡ ባሳዘኑት ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ፳፪፡
ያጠፋቸው ፡ ዘንድ ፡ ሳኦልን ፡ ላከው ።
እሱ ፡ ግን ፡ ንጉሣቸውን ፡ ከሞት ፡ አዳነው ፡ ፳፫፡
ብዙ ፡ ከብትንም ፡ ቆንጆዎችንና ፡ ሴቶችንም ፡
ያማሩ ፡ ጉልማሶችንም ፡ ከሞት ፡ አዳነ ፡ ነገሬን ፡
ንቋልና ፡ ትእዛዜንም ፡ አልሰማምና ፡ ስለዚህ ፡
ነገር ፡ እግዚአብሔር ፡ ነቢዩ ፡ ሳሙኤልን ፡
ሒደህ ፡ መንግሥቱን ፡ ክፈላት ።
ስለሱ ፡ ፈንታ ፡ በእስራኤል ፡ ላይ ፡ ይነግሥ ፡ ፳፬፡
ዘንድ ፡ የሰሜይ ፡ ልጅ ፡ ዳዊትን ፡ ቀባው ።
በእሱ ፡ ግን ፡ አንቆ ፡ የሚጥለው ፡ ጋኔንን ፡ ፳፭፡
አሰናብትበት ።
ፈቃዴን ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ መንግሥትን ፡ ብሰ ፳፮፡
ጠው ፡ እምቢ ፡ ብሏልና ፡ ፈቃዴን ፡ ማድረግ ፡
እምቢ ፡ ባለኝ ፡ ጊዜ ፡ ከሚገባው ፡ ከመንግሥቱ ፡
ሻርሁት ፡ አንተ ፡ ግን ፡ ሂደህ ፡ በወገኖቼ ፡ በእ
ስራኤል ፡ ላይ ፡ ያነገሠህን ፡ በጌትነቱ ፡ ዙፋን ፡
ላይ ፡ ያስቀመጠህ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንዲህን ፡
ቸል ፡ ትለዋለህን ፡ ብለህ ፡ ንገረው ፡ አለው ።
አንተ ፡ ግን ፡ ይህን ፡ ያህል ፡ ብዙ ፡ ክብርን ፡ ፳፯፡
ገናንነትንም ፡ የሰጠህ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አላወ
ቅህም ፡ በለው ፡ አለው ።
ነቢዩ ፡ ሳሙኤልም ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ወደ ፡ ሳኦል ፡ ፳፰፡
ሂዶ ፡ በማዕድ ፡ ተቀምጦ ፡ የአማሌቅ ፡ ንጉሥ ፡
አጋግም ፡ በግራው ፡ ተቀምጦ ፡ሳለ ፡ ወደሱ ፡ ገባ ።
ከብቱንና ፡ ሰውን ፡ ታጠፋ ፡ ዘንድ ፡ ያዘዘህ ፡ ፳፱፡
እግዚአብሔርን ፡ ፈጽመህ ፡ ለምን ፡ ቸል ፡ አል
ከው ፡ አለው ።
የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ንጉሡ ፡ ፈርቶ ፡ ከዙፋኑ ፡ ተነ ፴፡
ሥቶ ፡ ሳሙኤልን ፡ ተመለስልን ፡ ልብሱን ፡
ያዘው ፡ ሳሙኤልም ፡ መመለስን ፡ እምቢ ፡ አለው ፡
የሳሙኤል ፡ ልብስ ፡ ተቀደደ ።
ሳሙኤልም ፡ ሳኦልን ፡ እግዚአብሔር ፡ መንግ ፴፩፡
ሥትህን ፡ ከፈላት ፡ አለው ።
ዳግመኛም ፡ ሳኦል ፡ ሳሙኤልን ፡ በሕዝቡ ፡ ፊት ፡ ፴፪፡
አክብረኝ ፡ ይቅር ፡ ይለኝም ፡ ዘንድ ፡ በእግ
ዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ኃጢአቱን ፡ አስተሥርይ
ልኝ ፡ አለው ፡ የፈጠረው ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ቃል ፡ ፈርቷልና ፡ የሚሞት ፡ ንጉሡን ፡ ግን ፡
አልፈራውምና ፡ ሳሙኤልም ፡ በቃሉ ፡ መመ
ለስን ፡ እምቢ ፡ አለ ።

፴፫፤ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ያላመጠውን ፡ ሳይመጠው ፡
የአማሌቅ ፡ ንጉሥ ፡ አጋግን ፡ ወጋው ፡፡
፴፬፤ ሕገ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያፈረሰ ፡ ያንንም ፡ ሳኦ
ልን ፡ ጋኔን ፡ ያዘው ፡ እሱ ፡ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡
ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ስለሆነ ፡ እግዚአብሔር ፡ ኃጢ
አት ፡ የሠራ ፡ ንጉሥን ፡ አያፍረውምና ፡ ራሱ
ንም ፡ መታው ፡፡
፴፭፤ የማይፈሩት ፡ የመኳንንቱንና ፡ የነገሥታቱን ፡
ሥልጣን ፡ ሁሉ ፡ የሚሽር ፡ እሱ ፡ የፍጥረቱ ፡ ሁሉ ፡
ጌታ ፡ ነውና ፡ እሱን ፡ ግን ፡ የሚገዛው ፡ የለም ፡፡
፴፮፤ የዳዊት ፡ ወገን ፡ እየገነነ ፡ እየከበረ ፡ ይሄዳል ፡
የሳኦል ፡ ወገን ፡ ግን ፡ እየተዋረደ ፡ ይሄዳል ፡
ብሎ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ ከልጁና ፡ ከሳኦል ፡ መን
ግሥት ፡ አጠፋ ፡፡
፴፯፤ ስላሳዘነው ፡ በክፉ ፡ ሥራቸው ፡ ያሳዘኑት ፡ ወን
ጀለኞችንም ፡ ስለ ፡ አጠፋ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተበ
ቀሎ ፡ የሳኦልን ፡ ወገን ፡ ልጆች ፡ አጠፋ ፡ የእግ
ዚአብሔርን ፡ ጠላት ፡ የማይበቀል ፡ ሰው ፡ እሱ ፡
የእግዚአብሔር ፡ ጠላት ፡ ነውና ፡፡
፴፰፤ ተበቅሎ ፡ ማጥፋት ፡ ሲቻለው ፡ ሥልጣንም ፡
ሳለው ፡ ኃጢአተኛውን ፡ ተበቅሎ ፡ የማያጠ
ፋው ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ሕግ ፡ የማይጠብቅ ፡
ሰውን ፡ ተበቅሎ ፡ የማያጠፋው ፡ ሰው ፡ እሱ ፡
በውነት ፡ የእግዚአብሔር ፡ ጠላት ፡ ነውና ፡ የሳ
ኦልን ፡ ወገን ፡ ልጆች ፡ አጠፋ ፡፡

ምዕራፍ ፡ ፯ ፡፡

፩፤ አንተ ፡ ንጉሥም ፡ ብትሆን ፡ ገገርም ፡ ብት
ሆን ፡ አንተ ፡ ምን ፡ ቁም ፡ ነገር ፡ ነህ ፡፡
፪፤ ፈቃዱን ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ፡ በትእዛዙም ፡ ጸን
ተህ ፡ ትኖር ፡ ዘንድ ፡ ፍርዱንም ፡ ትፈራ ፡ ዘንድ ፡
ከለመኖር ፡ ወደ ፡ መኖር ፡ አምጥቶ ፡ የፈጠረህ ፡
እግዚአብሔር ፡ አይደለምን ፡ አንተ ፡ ባሮችህን ፡
እንድትቆጣቸው ፡ በላያቸውም ፡ እንደ ፡ ሠለጠ
ንህ ፡ እንደዚሁም ፡ ሁሉ ፡ አንተንም ፡ የሚቆጣህ ፡
በላይህም ፡ የሚሠለጥን ፡ እግዚአብሔር ፡ አለ ፡፡
፫፤ አንተ ፡ ኃጢአት ፡ የሠሩ ፡ ሰዎችን ፡ ያለ ፡ ርኅ
ራኄ ፡ እንድትመታ ፡ እንደዚህም ፡ ሁሉ ፡ አንተ
ንም ፡ የሚመታህ ፡ እስከ ፡ ዘለዓለም ፡ ድረስ ፡
መውጫ ፡ ወደሌለበት ፡ ወደ ፡ ገሃነምም ፡ የሚ
ያወርድህ ፡ እግዚአብሔር ፡ አለ ፡፡
፬፤ ያልተገዛልህን ፡ እጅ ፡ መንሻም ፡ ያላመጣልህን ፡
አንተ ፡ እንድትገርፍ ፡ አንተ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
እጅ ፡ መንሻ ፡ የማታገባ ፡ ለምንድነው ፡፡
፭፤ አንተ ፡ ይፈሩህ ፡ ዘንድ ፡ እንድትወድ ፡ የፈጠ
ረህ ፡ ወገኖቹንም ፡ በውነት ፡ ትጠብቅ ፡ ዘንድ ፡
በፍጥረቱ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ያነገሠህ ፡ እሱ ፡ ነውና ፡
ፈጣሪህ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የማትፈራው ፡ ለም
ንድነው ፡፡
፮፤ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሾመህ ፡ በሚገባውና ፡
በውነት ፡ ፍረድ ፡ እንጂ ፡ ፊት ፡ አይተህ ፡ ለታ
ናሽና ፡ ለታላቅ ፡ አታድላ ፡ ያለሱ ፡ ማንን ፡ ትፈ
ራለህ ፡ አምልኮቱንና ፡ ዘጠኙን ፡ ትእዛዝም ፡
ጠብቅ ፡፡
ውኃና ፡ እሳትን ፡ አቀረብሁልህ ፡ እጅህን ፡ ወደ ፡ ፯፤
ወደድኸው ፡ ጨምር ፡ ብሎ ፡ ሙሴ ፡ የእስራኤ
ልን ፡ ልጆች ፡ እንዳዘዛቸው ፡ ወደ ፡ ቀኝም ፡
ወደ ፡ ግራም ፡ አትሂድ ፡፡
ቃሉን ፡ ትሰማ ፡ ዘንድ ፡ ትእዛዙንም ፡ ታደርግ ፡ ፰፤
ዘንድ ፡ የምነግርህን ፡ ቃሉን ፡ ስማ ፡ በባሕር ፡
ማዶ ፡ ወይም ፡ በጥልቁ ፡ ማዶ ፡ ወይም ፡ በወ
ንዙ ፡ ማዶ ፡ አለች ፡ አያት ፡ ዘንድ ፡ ቃሉንም ፡
እሰማ ፡ ዘንድ ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ትእዛዙን ፡
አደርግ ፡ ዘንድ ፡ ማን ፡ ያመጣልኛል ፡ እን
ዳትል ፡፡
ሰምቼ ፡ አደርጋት ፡ ዘንድ ፡ ዳግመኛም ፡ ወደ ፡ ፱፤
ሰማይ ፡ ወጥቶ ፡ ያቺን ፡ የእግዚአብሔር ፡
ቃል ፡ ማን ፡ ያወርድልኛል ፡ እንዳትል ፡ በፍህ ፡
ልታስተምራት ፡ በጅህ ፡ ልትመጸውትባት ፡
እነሆ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ የቀረበ ፡ ነው ፡፡
መጽሐፉንም ፡ ካልሰማኸው ፡ ፈጣሪህ ፡ እግዚ ፲፤
አብሔርን ፡ አልሰማኸውም ፡ ሕጉንም ፡ ካልጠ
በቅህ ፡ እሱን ፡ አልወደድኸውም ፡ ትእዛዙንም ፡
አላደረግህም ፡፡
አንተም ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡ ትገባ ፡ ፲፩፤
ዘንድ ፡ አለህ ፡ ትእዛዙንም ፡ ካልወደድህ ፡ በው
ነት ፡ ትጠብቃቸው ፡ ዘንድ ፡ ከወገኖችህ ፡ ሁሉ ፡
ለይቶ ፡ ያከበረህ ፡ ያገነነህ ፡ የእግዚአብሔርንም ፡
ፈቃድ ፡ ካላደረግህ ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡
ትገባ ፡ ዘንድ ፡ አለህ ፡፡
ከሁሉ ፡ በላይ ፡ አደረገህ ፡ የፈጠረህ ፡ መንግሥ ፲፪፤
ትን ፡ የሰጠህ ፡ የፈጣሪህን ፡ ስም ፡ እያሰብክ ፡
በውነት ፡ በሚገባ ፡ ወገኖቹን ፡ ትገዛ ፡ ዘንድ ፡
በወገኖቹም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ አነገሠህ ፡፡
አንተን ፡ ከበደሉህ ፡ ሰዎች ፡ የምትገርፋቸው ፡ ፲፫፤
አሉ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሥራ ፡ እያሰብክ ፡ የም
ትምረውም ፡ አለ ፡ ልቡናህንም ፡ አንቅተህ ፡
በሚገባ ፡ የምትፈርድለት ፡ አለ ፡፡
በፊትህም ፡ በተከራከሩ ፡ ጊዜ ፡ ፊት ፡ አይተህ ፡ ፲፬፤
አታድላ ፡ ምድር ፡ ሁለንተናዋ ፡ ያንተ ፡ ገንዘብ ፡
ናትና ፡ ኃጢአተኛውን ፡ ሰው ፡ ትምረው ፡ ንጹ
ሑን ፡ ሰው ፡ ትበድለው ፡ ዘንድ ፡ ማማለጃ ፡
አትቀበል ፡፡
ፈቃዱን ፡ ካደረግህ ፡ እግዚአብሔር ፡ በዚህ ፡ ፲፭፤
ዓለም ፡ ዘመንህን ፡ ያበዛልሃል ፡ ብታሳዝነው ፡
ግን ፡ ዘመንህን ፡ ያሳንሰዋል ፡፡
ከሞትህ ፡ በኋላ ፡ እንድትነሣ ፡ በጎም ፡ ቢሆን ፡ ፲፮፤
ክፉም ፡ ቢሆን ፡ በሠራኸው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡
በፊቱ ፡ ቁመህ ፡ እንድትመረመር ፡ አስብ ፡፡
በጎ ፡ ሥራ ፡ ብትሠራ ፡ ደጋግ ፡ ነገሥታት ፡ በሚ ፲፯፤
ኖሩባቸው ፡ ብርሃን ፡ በመላባቸው ፡ ቤት ፡ በገ
ነት ፡ በመንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ ትኖራለህ ፡፡ እግዚ
አብሔር ፡ የጌትነትህን ፡ ሥልጣን ፡ አያፍርምና ፡
ክፉ ፡ ሥራ ፡ ብትሠራ ፡ ግን ፡ ክፉዎች ፡ ነገሥ
ታት ፡ በሚኖሩበት ፡ በሲኦል ፡ በገሃነም ፡ ትኖራ
ለህ ፡፡
አንተ ፡ ግን ፡ የመፈራትህን ፡ ገናንነት ፡ ያርበኛ ፲፰፤
ችህን ፡ ሽልማት ፡ የተሰቀለ ፡ ጋሻ ፡ ጦርህንም ፡

በየህ ፡ ጊዜ ፡ ፈረሶችህንም ፡ ከሥልጣንህ ፡
በታች ፡ ያሉ ፡ ጭፍሮችህንም ፡ ነጋሪትንም ፡
የሚመቱ ፡ በፊትህ ፡ በበገና ፡ የሚጫወቱትን ፡
ሰዎችን ፡ በየህ ፡ ጊዜ ።
፲፱፤ አንተ ፡ ግን ፡ ይኸንን ፡ ሁሉ ፡ በየህ ፡ ጊዜ ፡ ልቡ
ናህን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ታደርጋለህ ፡ ክሣደ ፡ ልቡና
ህንም ፡ ታጸናለህ ፡ ይኸን ፡ ሁሉ ፡ ክብር ፡ የሰ
ጠህ ፡ እግዚአብሔርንም ፡ አታስበውም ፡ ነገር ፡
ግን ፡ ይኸን ፡ ሁሉ ፡ ተው ፡ ባለህ ፡ ጊዜ ፡ አንተ ፡
የምትተወው ፡ አይደለህምን ።
፳፤ የሾመህን ፡ ሹመት ፡ ፈጽመህ ፡ ቸል ፡ ብለሃልና ፡
ጌትነትህንም ፡ ለሌላ ፡ ይሰጠዋል ።
፳፩፤ ድንገት ፡ ሞት ፡ ይመጣብሃልና ፡ በትንሣኤም ፡
ጊዜ ፡ ፍርድ ፡ ይደረጋልና ፡ የሰውም ፡ ሥራ ፡
ሁሉ ፡ ይመረመራልና ፡ ፈጽሞ ፡ ተመራምሮ ፡
ይፈረድብሃል ።
፳፪፤ የዚህን ፡ ዓለም ፡ ነገሥታት ፡ የሚያከብራቸው ፡
የለም ፡ እርሱ ፡ የውነት ፡ ዳኛ ፡ ስለሆነ ፡ በፍርድ ፡
ጊዜ ፡ ድኃና ፡ ባለጸጋ ፡ አንድነት ፡ ይቆማሉና ።
የዚህ ፡ ዓለም ፡ መኳንንት ፡ የሚመኩበት ፡ ዘው
ዳቸው ፡ ይወድቃል ።
፳፫፤ ፍርድ ፡ የተዘጋጀ ፡ ነው ፡ ነፍስም ፡ ትንቀጠቀ
ጣለች ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ የኃጥአንና ፡ የጻድቃን ፡
ሥራ ፡ ይመረመራል ።
፳፬፤ የሚሠወረውም ፡ የለም ። ሴት ፡ ለመውለድ ፡
በደረሰች ፡ ጊዜ ፡ በሆዷም ፡ ያለ ፡ ፅንስ ፡ ለመ
ወለድ ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ ማኅፀኗን ፡ ለመከል
ከል ፡ እንዳትችል ፡ ምድርም ፡ በርሷ ፡ ላይ ፡ ያሉ ፡
አዳሪዋን ፡ መከልከል ፡ አትችልም ፡ ትመልሳ
ለች ።
፳፭፤ ደመናዎችም ፡ እግዚአብሔር ፡ ወዳዘዛቸው ፡
በታ ፡ ወስደው ፡ እንዳያዘንሙ ፡ ዝናምን ፡
መከልከል ፡ እንዳይችሉ ፡ የእግዚአብሔርም ፡
ቃል ፡ ሁሉን ፡ ከለመኖር ፡ ወደ ፡ መኖር ፡ አም
ጥቶ ፡ ፈጥሮታልና ፡ ዳግመኛም ፡ የእግዚአብ
ሔር ፡ ቃል ፡ ሁሉን ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ አግብ
ቶታልና ፤ እንደዚሁም ፡ ሁሉ ፡ የትንሣኤ ፡
ጊዜ ፡ ከደረሰ ፡ በኋላ ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ እን
ዳይነሡ ፡ መሆን ፡ አይቻልም ።
፳፮፤ ከእግዚአብሔር ፡ አንደበት ፡ በሚወጣ ፡ ቃል ፡
ነው ፡ እንጂ ፡ ሰው ፡ የሚድን ፡ በእህል ፡ ብቻ ፡
አይደለም ፡ ብሎ ፡ ሙሴ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፤ ዳግ
መኛም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ሰውን ፡ ሁሉ ፡
ከመቃብር ፡ ያስነሣዋል ።
፳፯፤ እነሆ ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡
እንዲነሡ ፡ ታወቀ ።
፳፰፤ መኳንንትና ፡ ነገሥታት ፡ ስለሚሆኑ ፡ ፈቃዱን ፡
ስለሚያደርጉ ፡ ሰዎች ፡ ዳግመኛም ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ በዳግም ፡ ሕግ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡ ለጥፋት ፡
የሚቈጠሩበት ፡ ቀን ፡ ደርሷልና ፡ ፍርድ ፡ በሚ
ፈረድበት ፡ ቀን ፡ እግራቸውም ፡ በሚሰነከል
በት ፡ ጊዜ ፡ ተበቀዬ ፡ አጠፋቸዋለሁ ፡ አለ ።
፳፱፤ ዳግመኛም ፡ እግዚአብሔር ፡ ፍርዱን ፡ የሚያ
ውቁ ፡ ሰዎችን ፡ ፈጣሪያቸው ፡ እግዚአብሔር ፡
እኔ ፡ እንደ ፡ ሆንሁ ፡ እኔ ፡ እንድገድል ፡ እንዳ
ድን ፡ እወቁ ፡ እወቁ ፡ አላቸው ።
በመከራው ፡ እቀሥፋለሁ ፡ ይቅር ፡ እላለሁ ፡ ፴፤
ወደ ፡ ሲኦል ፡ አወርዳለሁ ፡ ዳግመኛም ፡ ወደ ፡
ገነት ፡ አወጣለሁ ፡ ከሥልጣኔም ፡ የሚያመልጥ ፡
የለም ፡ አላቸው ።
ሕጉን ፡ ስላልጠበቁ ፡ መኳንንትና ፡ ነገሥታት ፡ ፴፩፤
እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡ ምድራዊ ፡ መን
ግሥት ፡ ኃላፊ ፡ ነውና ፡ ከጢት ፡ እስከ ፡ ማታም ፡
ድረስ ፡ ያልፋልና ፡ ዘለዓለም ፡ ጸንቶ ፡ ወደሚ
ኖር ፡ ወደ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ ትገቡ ፡ ዘንድ ፡
ሥርዓቴና ፡ ሕጌን ፡ ጠብቁ ፡ አለ ።
እግዚአብሔር ፡ ጻድቃንን ፡ መጥራቱ ፡ ለክብር ፡ ፴፪፤
ኃጥአንንም ፡ ለመከራ ፡ ነውና ፤ ኃጢአተኛውን ፡
ያጕስቍላል ፡ ጻድቃንን ፡ ግን ፡ ያከብራል ።
ፈቃዱን ፡ ያላደረገ ፡ ሰውን ፡ ይኸረዋል ፡ ፈቃ ፴፫፤
ዱን ፡ ያደረገ ፡ ሰውን ፡ ግን ፡ ይሾመዋል ።

ምዕራፍ ፡ ፰ ።

የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ የሚነሡበትን ፡ ነገር ፡ ስማኝ ፡ ፩፤
ልንገርህ ፡ ተክልን ፡ ይተክላሉ ፡ ይለመልማሉ ፡
ወይንም ፡ አረግ ፡ ያወጣል ፡ እግዚአብሔር ፡
ፍሬውን ፡ እምነበ ፡ አልቦ ፡ ያመጣዋልና ፡ ከሱ ፡
ጠጅ ፡ ይጥላሉ ።
ያች ፡ የተክልከት ፡ ተክል ፡ ታናሽ ፡ እንደ ፡ ነበ ፪፤
ረች ፡ ዛሬ ፡ ግን ፡ ጫፎችን ፡ ፍሬና ፡ ቅጠልን ፡
እንዳወጣች ፡ አስተውል ።
እግዚአብሔር ፡ ከመሬትና ፡ ከውኃ ፡ ከሁለቱ ፡ ፫፤
ሥርዋን ፡ ያጠጣዋል ።
እንጨቷን ፡ ግን ፡ ከእሳትና ፡ ከነፋስ ፡ ይመግበ ፬፤
ቸዋል ፡ ሥር ፡ ለቅጠል ፡ ውኃን ፡ ታጠጣለች ፡
መሬትም ፡ ለእንጨቶች ፡ ጽናትን ፡ ትሰጣለች ።
እግዚአብሔር ፡ የፈጠረው ፡ ነፍስ ፡ ግን ፡ በመ ፭፤
ከከላቸው ፡ ፍሬን ፡ እንዲያፈሩ ፡ ያደርጋል፡
የሞቱ ፡ ሰዎችም ፡ መነሣት ፡ እንደዚሁ ፡ ነው ።
ነፍስ ፡ ከሥጋ ፡ በተለየች ፡ ጊዜ ፡ እየራሱ ፡ ሂዷ ፮፤
ልና ፡ ከመሬትና ፡ ከውሃ ፡ ከነፋስና ፡ ከእሳት ፡
ከራቱ ፡ ባሕርያት ፡ ነፍሳትን ፡ ሰብስቦ ፡ አለ ።
መሬት ፡ ባሕርይ ፡ ግን ፡ በባሕርዩዋ ፡ ጸንታ ፡ ፯፤
ኖረች ፡ መሬትንም ፡ ሆነች ፡ ውሃ ፡ ባሕርዩም ፡
በባሕርዩዋ ፡ ጸንታ ፡ ኖረች ፡ ውሃ ፡ ሆነች ።
ነፋስ ፡ ባሕርይም ፡ በባሕርዩዋ ፡ ጸንታ ፡ ኖረች ፡ ፰፤
ነፋስ ፡ ሆነች ፡ እሳት ፡ ባሕርይም ፡ በባሕርዩዋ ፡
ጸንታ ፡ ኖረች ፡ የሚሞቅ ፡ እሳት ፡ ሆነች ።
እግዚአብሔር ፡ ከሥጋ ፡ የለየት ፡ ነፍስ ፡ ግን ፡ ፱፤
ወደ ፡ ፈጣሪዋ ፡ ተመለሰች ፡ በወደደ ፡ ጊዜ ፡
ከሥጋ ፡ አዋሕዶ ፡ እስኪያነሣት ፡ ድረስ ፡ በወደ
ደው ፡ በታ ፡ በገነት ፡ ያኖራታል ።
የጻድቃንን ፡ ነፍሶች ፡ በብርሃን ፡ ቤት ፡ በነገት ፡ ፲፤
ያኖራቸዋል ፡ የኃጢአተኞች ፡ ነፍሶችን ፡ ግን ፡
ያወጣቸው ፡ ዘንድ ፡ እስከ ፡ ወደደበት ፡ ጊዜም ፡
ድረስ ፡ በጨለማ ፡ ቤት ፡ በሲኦል ፡ ያኖራቸዋል ።
ተሰብስበው ፡ አንድ ፡ አካል ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ፲፩፤
እግዚአብሔር ፡ ነቢዩ ፡ ሕዝቅኤልን ፡ ከራቱ ፡

ማዕዘን ፡ ነፋሳትን ፡ ጥራ ፡ አለው ።
፲፪ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ በንድ ፡ ቃል ፡ በተናገረ ፡ ጊዜ ፡
ነፋሳት ፡ ከራቱ ፡ ማዕዘን ፡ ተሰበሰቡ ።
፲፫ ውኃ ፡ በሕርይም ፡ ልምላሚን ፡ አመጣ ፡ ዳግመ
ኛም ፡ እሳት ፡ ባሕርይ ፡ እሳትን ፡ አመጣ ።
፲፬ መሬት ፡ በሕርይም ፡ ዳግመኛ ፡ መሬትን ፡ አመጣ ፡
ነፋስ ፡ በሕርይም ፡ ነፋስን ፡ አመጣ ።
፲፭ እግዚአብሔርም ፡ ነፍስን ፡ ከኖረበት ፡ ቦታ ፡ ከገ
ነት ፡ አመጣ ፡ በንድ ፡ ቃል ፡ ተሰበሰቡ ፡ ትንሣ
ኤም ፡ ተደረገ ።
፲፮ ዳግመኛም ፡ በንተ ፡ ዘንድ ፡ ያለ ፡ ምሳሌን ፡ አሳ
ይሃለሁ ፡ ቀኑ ፡ ይመሽል ፡ ትተኛለህ ፡ ሌሊቱ ፡
ይነጋል ፡ ከመኝታህም ፡ ትነሣለህ ፡ አንተ ፡ ግን ፡
በተኛህ ፡ ጊዜ ፡ የሞትህ ፡ ምሳሌ ፡ ነው ።
፲፯ በነቃህም ፡ ጊዜ ፡ የመነሣትህ ፡ ምሳሌ ፡ ነው ፡
ጨለማ ፡ ሸፍኗቸዋልና ፡ ሁለንተናው ፡ ጨለማ ፡
የሆነ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ የሚተኛበት ፡ ሌሊቱ ፡ ግን ፡
የዚህ ፡ ዓለም ፡ ምሳሌ ፡ ነው ።
፲፰ ጨለማ ፡ የሚወገድበት ፡ በዓለሙም ፡ ሁሉ ፡
ብርሃን ፡ የሚሆንበት ፡ ሰውም ፡ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡
እርሻው ፡ የሚሠማራበት ፡ የጧት ፡ በርሃን ፡
ግን ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ ምሳሌ ፡ ነው ።
፲፱ ሰው ፡ የሚቃደስበት ፡ ይህች ፡ መንግሥት ፡ ሰማ
ይም ፡ እንደዚህ ፡ ናት ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ ትን
ሣኤ ፡ እንደዚህ ፡ ነው ፡ ይህ ፡ ዓለም ፡ ኃላፊ ፡
ነውና ፡ የሌሊቱ ፡ ምሳሌ ፡ ነው ።
፳ ዳዊትም ፡ ምሳሌውን ፡ በፀሐይ ፡ አኖረ ፡ ብሎ ፡
እንደ ፡ ተናገረ ፡ ፀሐይ ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ ያበራ
ልና ፡ የመንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ ምሳሌ ፡ ነው ።
፳፩ ዛሬ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ፀሐይ ፡ እንዲያበራ ፡ እሱ ፡
ክርስቶስም ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ሐዲስ ፡ በሚሆን ፡
በመንግሥት ፡ ሰማይ ፡ እንደ ፡ ፀሐይ ፡ ያበራል ፡
የማይገባ ፡ ፀሐይ ፡ የማይጠፋም ፡ ፋና ፡ እኔ ፡
ነኝ ፡ ብሏልና ፡ እሱ ፡ እግዚአብሔር ፡ ብርሃንዋ ፡
ነው ።
፳፪ ዳግመኛም ፡ የሞቱትን ፡ ሰዎች ፡ ፈጥኖ ፡ ያስነ
ሣቸዋል ፡ ከምትዘራው ፡ አንተም ፡ ከምትድን
በት ፡ ከምግብህ ፡ ዳግመኛም ፡ አንዲት ፡ ምሳሌ ፡
አመጣልሃለሁ ፡ የስንዴም ፡ ቅንጣት ፡ ቢሆን ፡ የገ
ብስም ፡ ቅንጣት ፡ ቢሆን ፡ የምስርም ፡ ቅንጣት ፡
ቢሆን ፡ በምድር ፡ የሚዘራ ፡ የሰውም ፡ ዘር ፡
ሁሉ ፡ ካልፈረሰ ፡ ካልበሰበሰ ፡ የሚበቅል ፡ የለም ።
፳፫ እንደምታየው ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ሥጋ ፡ በፈረ
ሰም ፡ በበሰበሰም ፡ ጊዜ ፡ ግዘፍን ፡ ከቀበርበቱ ፡
ጋራ ፡ መሬት ፡ ይበላዋል ።
፳፬ ግዘፉንም ፡ መሬት ፡ በበላው ፡ ጊዜ ፡ የቅንጣት ፡
ሰባተኛ ፡ ያህል ፡ ሆኖ ፡ ይበቅላል ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ እንደ ፡ ወደደ ፡ ዝናም ፡ የያዘ ፡ ነፋስን ፡
ይሰጣል ፡ ሥርም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ በቅላ ፡ ቅጠ
ልን ፡ ታወጣለች ።
፳፭ እርሷም ፡ ከፈረሰች ፡ ከበሰበሰች ፡ መብቀል ፡
አትችልም ፡ ከበቀለች ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ብዙ ፡ ዝር
ዝር ፡ ታወጣለች ።
፳፮ ላደገው ፡ ለዚያ ፡ ለዝርዝሩም ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፈቃድ ፡ ፍሬ ፡ ይሰጠዋል ፡ ግዘፉንም ፡ ገለባ ፡
ያለብሰዋል ።
የዘራኸው ፡ ዘር ፡ ቅንጣቱ ፡ እንደበዛ ፡ መጠን ፡ ፳፯
አይ ፡ እንጂ ፡ ብሩና ፡ ቅጠሉ ፡ ምርቁና ፡ ገለ
በው ፡ አይቆጠርልህም ።
የማያውቅ ፡ ደንቆሮ ፡ አትሁን ፡ ዘርህንም ፡ እን ፳፰
ደበዛ ፡ አይ ፡ እንደዚህም ፡ ሁሉ ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡
የሚነሡትን ፡ መነሣት ፡ እንደ ፡ ሥራቸውም ፡
ፍዳቸውን ፡ እንዲቀበሉ ፡ አስብ ።
ስንዴ ፡ ብትዘራው ፡ ገብስ ፡ ሆኖ ፡ ገብስ ፡ ብትዘ ፳፱
ራው ፡ ስንዴ ፡ ሆኖ ፡ እንዳይበቅል ፡ ስማኝ ፡
ልንገርህ ፡ ዳግመኛም ፡ እንዳይበቅል ፡ ስንዴ ፡
ብትዘራ ፡ ገብስ ፡ ትሰበስባለህን ፡ ሬጦ ፡ ብትዘራ ፡
ተልባ ፡ ትሰበስባለህን ።
ከትክልስ ፡ ወገን ፡ በለስ ፡ ብትተክል ፡ በውኑ ፡ ፴
ለውዝ ፡ ሆኖ ፡ ይበቅልልሃልን ፡ ገውዝስ ፡ ብት
ተክል ፡ ወይን ፡ ሆኖ ፡ ይበቅልልሃልን ።
የጣፈጠውን ፡ ፍሬ ፡ ብትተክል ፡ የመረረ ፡ ሆኖ ፡ ፴፩
ይበቅልልሃልን ፡ የመረረውንስ ፡ ፍሬ ፡ ብት
ተክል ፡ የጣፈጠውን ፡ መሆን ፡ ይቻለዋልን ።
እንደዚሁስ ፡ ሁሉ ፡ ኃጢአተኛ ፡ ቢሞት ፡ በት ፴፪
ንሣኤ ፡ ጊዜ ፡ ጻድቅን ፡ ሆኖ ፡ መነሣት ፡ ይቻላ
ልን ፡ ጻድቅ ፡ ሰውስ ፡ ቢሞት ፡ በትንሣኤ ፡ ጊዜ ፡
ኃጢአተኛ ፡ ሆኖ ፡ መነሣት ፡ ይቻላልን ፡ ሁሉም ፡
እንደሥራው ፡ ፍዳውን ፡ ይቀበላል ፡ እንጂ ፡
እንደ ፡ ኃጢአቱ ፡ እንደ ፡ እጁም ፡ ሥራ ፡ ፍዳ
ውን ፡ ይቀበላል ፡ እንጂ ፡ በባልንጀራው ፡ ኃጢ
አት ፡ የሚፈረድበት ፡ የለም ።
የደጋ ፡ ዛፍ ፡ ይተከላል ፡ ረጃጅም ፡ ቅርንጫፎ ፴፫
ችንም ፡ ያወጣል ፡ ፈጽሞ ፡ ይደርቃል ፡ እንጂ ፡
የሰማይ ፡ ዝናም ፡ ካልዘነመ ፡ ቅጠሉ ፡ አይለመ
ልምም ።
ዝግባውም ፡ የክረምት ፡ ዝናም ፡ በርሱ ፡ ካል ፴፬
ወረደ ፡ ከሥሩ ፡ ይነቀላል ።
እንደዚሁም ፡ ሁሉ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ታዝዞ ፡ ፴፭
የደኅንነት ፡ ጠል ፡ ካልወረደላቸው ፡ የሞቱ ፡
ሰዎች ፡ አይነሡም ።

ምዕራፍ ፡ ፱ ።

የደጋ ፡ ተራሮችና ፡ የጌላቡሄ ፡ አውራጃዎች ፡ ፩
ከእግዚአብሔር ፡ ታዝዞ ፡ ይቅርታ ፡ ዝናም ፡ ካል
ዘነመላቸው ፡ ለአውሬዎችና ፡ ለእንስሳዎች ፡
ሣርን ፡ አያበቅሉም ።
የኤላም ፡ ተራራዎችና ፡ የገለዓድ ፡ ተራራዎ ፪
ችም ፡ ለሚሠመሩ ፡ ለበጎችና ፡ ለፍየሎች ፡ ለፊ
ቆና ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ላሉ ፡ እንስሳትም ፡ ለዋሊያ
ዎችና ፡ ለቶራትም ፡ የለመለመ ፡ ቅጠልን ፡ አይ
ሰጡም ።
እንደዚሁም ፡ ስሕተትና ፡ ወንጀልን ፡ አስቀ ፫
ድሞ ፡ ገንዘብ ፡ ያደረጉት ፡ ተጠራጣሪና ፡ ወንጀ
ለኞች ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ታዝዞ ፡ ይቅርታና ፡
ጠል ፡ አልወረደላቸውም ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ አይ
ነሡም ፡ ጣዖት ፡ የሚያመልኩና ፡ ሥር ፡ የሚ
ምሱ ፡ ነገር ፡ ሠርተው ፡ የሚያጣሉ ፡ ዲማስና ፡

ቆጵሮስም ።
፬፤ ሥር፡የሚያምሱና፡ጥንቈላንም፡የሚጠነቍሉ፡
ሰውንም፡የሚያጋድሉ ።
፭፤ ከሕግም ፡ ወጥተው ፡ የሚሰስኑ ፡ በጣዖታቸው ፡
የሚያምኑ ፡ የሚያንና ፡ የአቱና ፡ ሰዎችም ፡
መስንቆንና ፡ ከበሮን ፡ እየመቱ ፡ በገናም ፡ እየ
ደረደሩ ፡ የሚጫወቱላቸውና ፡ የሚዘፍኑላቸ
ውም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ታገዘ ፡ የይቅርታ ፡
ጠል ፡ ከልወረደላቸው ፡ አይነሡም ።
፮፤ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ በሚነሡበት ፡ ቍርጥ ፡ ፍርድ ፡
በሚደረግበት ፡ ቀን ፡ የሚፈረድባቸው ፡ እነዚህ ፡
ናቸው ፡ እንጂ ፡ ራሳቸውን ፡ የሚያድኑ ፡ በኝ
ቸው ፡ ሥራ ፡ የሚሰስኑ ፡ ሰዎች ፡ በጣዖታቸው ፡
ይስታሉ ።
፯፤ አንተ ፡ ልበ ፡ በክና ፡ ደንቆሮ ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡
የማይነሡ ፡ ይመስልሃልን ።
፰፤ ሙታን ፡ ሊነሡበት ፡ በመላእክት ፡ አለቃ ፡ በቅ
ዱስ ፡ ሚካኤል ፡ አንደበት ፡ መለከት ፡ በተነፋ ፡
ጊዜ ፡ ሳትነሣ ፡ በመቃብር ፡ አትቀርምና ፡ እን
ዲህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ አታስብ ።
፱፤ ከረፍቶችና ፡ ተራሮች ፡ ይተክከላሉ ፡ ጥርጊያ ፡
ጐዳናም ፡ ይሆናሉ ።
፲፤ ለሥጋዊ ፡ ሁሉም ፡ ትንሣኤ ፡ ይደረጋል ።

ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩፤ ነገር ፡ ግን ፡ እንዲህ ፡ ካልሆነ ፡ የቀደሙ ፡ ሰዎች ፡
ከአዳም ፡ ጀምሮ ፡ ከሴትና ፡ ከአቤል ፡ ከሴምና ፡
ከኖኅ ፡ ከይስሐቅና ፡ ከአብርሃም ፡ ከዮሴፍና ፡
ከያዕቆብ ፡ ከአሮንና ፡ ከሙሴም ፡ ጀምሮ ፡ በአ
ባቶቻቸው ፡ መቃብር ፡ ይቀበሩ ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡
እንጂ ፡ በሌላ ፡ ቦታ ፡ ይቀበሩ ፡ ዘንድ ፡ ያልወ
ደዱ ፡ ለምንድነው ።
፪፤ በትንሣኤ ፡ ጊዜ ፡ ከዘመዳቸው ፡ ጋራ ፡ አንድነት ፡
ሊነሡ ፡ አይደለምን ፡ አጥንታቸውስ ፡ ጣዖት ፡
ከሚያመልኩ ፡ ከክፉዎች ፡ ከአረማውያንም ፡
አጥንት ፡ ጋራ ፡ እንዳይቈጠር ፡ አይደለምን ፡
በሌላ ፡ ቦታ ፡ ይቀበሩ ፡ ዘንድ ፡ ያልወደዱ ፡ ለም
ንድነው ።
፫፤ አንተ ፡ ግን ፡ እልፍ ፡ እልፍ ፡ ሆነው ፡ በንድ ፡
መቃብር ፡ የተቀበሩ ፡ ሰውነታቸውም ፡ የፈረሰ ፡
የበሰበሰ ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ ከሞቱ ፡ በኋላ ፡ እን
ዴት ፡ ይነሣሉ ፡ እያልህ ፡ ልቡናህን ፡ አታስት ።
፬፤ ወደ ፡ መቃብርም ፡ በየህ ፡ ጊዜ ፡ አፍኝ ፡ ሙሉ ፡
መሬት ፡ አይገኝም ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ እንዴት ፡
ይነሣሉ ፡ እያልክ ፡ በልቡናህ ፡ ድንቁርና ፡ ይህ
ንን ፡ ትናገራለህ ።
፭፤ አንተ ፡ የዘራኸው ፡ ዘር ፡ አይበቅልም ፡ ትላለ
ህን ፡ አንተ ፡ የዘራኸው ፡ ዘር ፡ ስንኳ ፡ ይበቅ
ላል ።
፮፤ እንደዚሁም ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔር ፡ የዘራቸው ፡
ነፍሳት ፡ ፈጥነው ፡ ይነሣሉ ፡ እሱ ፡ ሰውን ፡ በው
ነቱ ፡ ከለመኖር ፡ ወደ ፡ መኖር ፡ አምጥቶ ፡ ፈጥ
ሮታልና ፡ በምታድን ፡ ቃሉ ፡ ፈጥኖ ፡ ያስነሣቸ
ዋል ፡ ማስነሣቱን ፡ አያዘገይም ።
ዳግመኛም ፡ ከመኖር ፡ በሞት ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ፯፤
መልሶታልና ፡ ዳግመኛስ ፡ ከሞት ፡ ወደ ፡ ሕይ
ወት ፡ መመለስ ፡ አይቻለውምን ።
እግዚአብሔር ፡ ማዳን ፡ ማንሣት ፡ ይቻለዋል ። ፰፤

ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

አርሞን ፡ ጠሩች ፡ አምበዎቹም ፡ ፈረሱ ፡ እግ ፩፤
ዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ክፋታቸው ፡ በእጃቸውም ፡
እንደ ፡ ሠሩት ፡ ሥራ ፡ ፍዳውን ፡ አምጥቶባቸዋ
ልና ፡ በኢዮምያስና ፡ በዛብሎን ፡ ጣዖቶቹን ፡
የሚያመልኩ ፡ ሰዎች ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ ይዋረዳሉ ፡
በሕያንነታቸው ፡ በሠሩት ፡ እስኪያረጁም ፡
ድረስ ፡ ባልተወት ፡ ስለ ፡ ጣዖታቸውና ፡ ስለ ፡
ክፋታቸው ፡ የሚፈርድባቸው ፡ እግዚአብሔር ፡
ቀርቧልና ፡ ሲዮናና ፡ ጢሮስ ፡ ያለቅሳሉ ።
ኃጢአትንና ፡ መዳራትን ፡ ገዘሙትን ፡ ስለ ፡ ሠሩ ፡ ፪፤
ጣዖትንም ፡ ስላመለኩ ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ተበቅሎ ፡ ያጠፋቸዋል ፡ በፈጣሪያ
ቸው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ትእዛዝ ፡ ጸንተው ፡
አልኖሩምና ፡ የይሁዳም ፡ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ይጐ
ሰቍላሉ ።
ነቢያትን ፡ በመግደልና ፡ በተድላ ፡ በደስታ ፡ ፫፤
ጸንታ ፡ ኖረች ፡ እንጂ ፡ በዘጠኙ ፡ ሕግጋትና ፡
በአምልኮቱ ፡ ጸንታ ፡ አልኖረችምና ፡ ሙታን ፡
በሚነሡበት ፡ ጊዜ ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ኃጢአቷ ፡
ይገለጣል ።
የዚያን ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ በባሕርዩ ፡ ጥበቡ ፡ ፬፤
ይመረምራታል ፡ በሕያንነቷ ፡ ዘመን ፡ በሠራ
ችው ፡ ኃጢአቷ ፡ ሁሉ ፡ ተበቅሎ ፡ ያጠፋታል ፡
ከቆንጆነቷ ፡ ዘመን ፡ ጀምሮ ፡ እስከታረጅ ፡
ድረስ ፡ ኃጢአት ፡ መሥራቷን ፡ አልተወችም ።
በኃጢአታቸው ፡ ጸንተው ፡ እንደ ፡ ኖሩ ፡ እንደ ፡ ፭፤
ቀደሙ ፡ አበቶቿ ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ገብታ ፡
ትቢያ ፡ ሆነች ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ሕግ ፡ ያፈ
ረሱ ፡ ሰዎችን ፡ በትንሣኤ ፡ ጊዜ ፡ ተበቅሎ ፡ ያጠ
ፋቸዋል ።
የሕጋቸው ፡ ማደሪያ ፡ ልቡናቸው ፡ የሰዶም ፡ ፮፤
ሕግ ፡ ማደሪያ ፡ ሆነ ፡ ብሎ ፡ ሙሴ ፡ ስለነርሳቸው ፡
ተናግሯልና ፡ ይፈረድባቸዋል ።
ወገናቸውም ፡ የገሞራ ፡ ወገን ፡ ነው ፡ ሕጋቸ ፯፤
ውም ፡ የሚያጠፋ ፡ ነው ፡ ሥራቸውም ፡ ክፉ ፡
ነው ።
ሕጋቸውም ፡ የሚያጠፋ ፡ የበብ ፡ መርገዝ ፡ ከዚ ፰፤
ያውም ፡ ዘንድ ፡ የሚያጠፋ ፡ የፉኝት ፡ መርገዝ ፡
ነው ።

ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

የኢየሩሳሌም ፡ ልጅ ፡ ይህ ፡ ኃጢአትሽ ፡ እንደ ፡ ፩፤
ገሞራና ፡ እንደ ፡ ሰዶም ፡ ኃጢአት ፡ ነውና ፡
የኢየሩሳሌም ፡ ልጅ ፡ በነቢይ ፡ የተነገረ ፡ መከ
ራሽ ፡ ይህ ፡ ነው ።
መከራሽም ፡ እንደ ፡ ገሞራና ፡ እንደ ፡ ሰዶም ፡ ፪፤
መከራ ፡ ነው ፡ የሕግ ፡ ማደሪያ ፡ ልቡናቸውም ፡
በገዘሙትና ፡ በትዕቢት ፡ ጸና ።

፫፤ ያለገዘሙትና፡ያለትዕቢት፡ዝናም፡በቀር፡ያለኃ
ጢአትና፡ያለበደል፡የሰው፡ደም፡ከማፍሰስና፡
ከመቀማት ፡ የፈጣሪያቸው ፡ የእግዚአብሔር
ንም ፡ ስም ፡ ከመዘንጋት ፡ በቀር፡የሕግ፡ልቡና፡
ማደሪያቸው ፡ በሚለመልም ፡ ገንዘብ ፡ የይቅ
ርታና፡የትሕትና፡ዝናም፡ከልቡናቸው፡አል
ዘነመም ።
፬፤ ከክፉ ፡ ሥራቸውና ፡ ከጣዖታቸው ፡ በቀር ፡
ፈጣሪያቸው፡እግዚአብሔርንም፡አላወቁም፡
በእጃቸውም፡ሥራ፡ደስ ፡ ይላቸዋል ፡ በወን
ድና፡በከብትም፡ይሰስናሉ ።
፭፤ ምሥጢር፡እንዳያዩ፡ዓይነ፡ልቡናቸው፡ታው
ሯልና ፡ እንዳይሰሙ ፡ እግዚአብሔር፡የሚወ
ደው፡ፈቃዱንም፡እንዳያደርጉ፡ጆሯቸውም፡
ደንቍሯልና፡በሥራቸው ፡ እግዚአብሔርን፡
አላወቁም፡ልቡናቸውም፡እንደ፡ሰዶም፡ሕግ፡
ማደሪያ፡ነው።ወገናቸውም፡የጣፈጠ፡ፍሬን፡
የሚያፈራ፡የገሞራ፡ወይን፡ወገን ።
፮፤ ከተሠራበት ፡ ቀን፡ጀምሮ፡በርግማን፡ጸንቷ
ልና ፡ መሠረቱም፡በጥፋት፡ዘመን፡ሆኗልና፡
ሥራቸውንም ፡ ቢመረምሩት ፡ የሚገድል ፡
መርዝ፡ሆነ ።
፯፤ የሕጋቸው፡ማደሪያ፡ልቡናቸው፡በኃጢአት፡
ሥራ ፡ ጸንቷልና ፡ ሰውነታቸው ፡ ኃጢአት ፡
ለማሠራት ፡ በሚናደድ ፡ በሰይጣን ፡ ሥራ ፡
ጸንቷልና፡ለሕጋቸው፡ማደሪያ፡ለልቡናቸው፡
ሁለጊዜ፡በጎ፡ሥራ፡የለውም ።
፰፤ አፍርቶም ፡ በተጠመቀ ፡ ጊዜ ፡ (በተመረ ፡)
ለመቅሠፍትና፡ለጥፋት፡ሆነ፡የጠጡትንም፡
ሰዎች ፡ ልቡናቸውንም ፡ ያጸናዋል ፡ እኔንም፡
የሚያጠፉ ፡ የሚያጺይፉ ፡ ከእግዚአብሔር ፡
የራቁ፡ሰዎችን፡ያደርጋቸዋል ።
፱፤ ክፉ ፡ በሆነ ፡ ሥራው ፡ ጸንተው ፡ ይኖራሉና፡
የዲያብሎስም፡ማደሪያ፡ያደርጋቸዋል፡ቤተ፡
እስራኤልም፡ለጣዖቱ፡የተሠዋውን፡መብላት፡
ተጀመረበት፡ወደ፡ተራራዎቹም፡ወደ፡ዛፎ
ቹም፡ትወጣለች ።
፲፤ በዙሪያዋ ፡ ያሉ ፡ አሕዛብ ፡ የሚያመልኩት ፡
ጣዖቱንም፡ታመልከዋለች፡ከክፉ፡ለይተው፡
በጎ፡ሥራን፡ለማያውቁ፡ለአጋንንትም፡ሴቶች፡
ልጆቿንና፡ወንዶች፡ልጆቿን ።
፲፩፤ ንጹሕ ፡ ደምንም ፡ ያፈሳሉ ፡ ከሰዶም ፡ ወይን ፡
ለዘላለም ፡ ፍልቅ ፡ አድርገው ፡ ለጣዖቱ፡ያፈ
ሳሉ ።
፲፪፤ ኢሎፍላውያን፡የሚያመልኩት፡ዳጐንንም፡
አክብራ ፡ ታመልካለች ፡ ለትሠዋላቸውም ፡
አጋንንት፡ባስተማሯት፡በስንፍናቸውና፡ወይ
ኑን፡ፍልቅ፡አድርገው፡በማፍሰሳቸው፡ደስ፡
ይላት፡ዘንድ፡ከመንጋዎቿና፡ከሰቡት፡ላሞቿ፡
ትሠዋለታለች ፡ ፈቃዳቸውንም ፡ ታደርግ ፡
ዘንድ ።
፲፫፤ በየጊዜው፡የሚመግቡት፡ከሕፃንነቷ፡ጀምሮ፡
እስከ፡ቍንጅናዋ፡ዘመን፡ድረስ፡ዳግመኛም፡
እስከ፡እርጅናዋ፡ዘመን፡ድረስ፡ዳግመኛም፡
እስከ ፡ እርጅናዋ ፡ እስከምትሞትበት ፡ ቀን ፡
ድረስ ፡ ተከባክበ ፡ ያሳደጋት ፡ ፈጣሪዋ ፡ እግ
ዚአብሔርን፡እንዳታውቅ፡አጋንንት፡በስተ
ማሯት ፡ በስንፍናቸው ፡ ደስ ፡ ይላት፡ዘንድ ፡
ትሠዋለታለች ።
ዳግመኛም፡ተበቅዬ፡በትንሣኤ፡ጊዜ፡እፈር ፲፬፤
ድብታለሁ፡ወደ፡ሐኔም፡አልተመለስችምና፡
በትእዛዜም፡ጸንታ፡አልኖረችምና፡በገሃነም፡
የምትኖርበት፡ጊዜዋ፡እስከ፡ዘለዓለም፡ድረስ፡
ይሆናል ።
በውነት፡ፈጣሪዎች፡ከሆኑ፡እሷን፡ተቈጥቼ፡ ፲፭፤
ባጠፋሁ ፡ ጊዜ ፡ ከሷም ፡ ጋር፡የሚሰስኑ፡ከሀ
ናት፡ጣዖቱን፡ሁሉ፡ባራቅሁ፡ጊዜ፡ጣዖቶቿ፡
ከሷ ፡ ጋራ ፡ ተነሥተው ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡ ወር
ደው፡ያድኗት ።
በንዋየ፡ቅድሳትና፡በማደሪያዬ፡በቤተ፡መቅ ፲፮፤
ደስ፡ኃጢአትና፡ስድብ፡እንዳደረገች፡በዚህ፡
ሁሉ፡የጐሰቈለችን፡አደረግኋት ።
እነሆ ፡ ይህች ፡ የእግዚአብሔር፡ወገን፡ናት ፡ ፲፯፤
የእስራኤል ፡ ፈጣሪ፡እግዚአብሔርም ፡ ማደ
ሪያ ፡ ናት ፡ ከተለዩ ፡ የተለየች ፡ የገናናው ፡
ንጉሥ፡አገር፡ኢየሩሳሌምም፡የልዑል፡እግ
ዚአብሔር፡የስሙ፡ማደሪያ፡ናት፡ሲኋት፡
በሷ፡የተጠራ፡ስሜን፡እንዳሳዘነች፡የጐስቈ
ለችን፡አደረግኋት ።
እሷ፡በርያዬ፡እንደ፡ሆነች፡እኔም ፡ ጌታዋ ፡ ፲፰፤
እንደ፡ሆንኩ፡በኔ፡ትመካለች፡እንደ፡ወንጀ
ለኛ፡ትጠቃቀስብኛለች፡እንጂ፡ጌታዋ፡እንደ፡
መሆኔ፡የምትፈራኝ፡ፈቃዴንም ፡ የምታደ
ርግ፡አይደለችም ።
ከኔ፡ያርቋት፡ዘንድ፡ለማሳት፡መሰናክል፡ሆኑ ፲፱፤
ባት ፡ እንጂ ፡ ለማይመግቧት፡ለማያለብሷት፡
ለሌሎች፡ጣዖቶች፡ትገዛለች ።
መሥዋዕት፡ትሠዋላቸዋለች፡መሥዋዕቱንም፡ ፳፤
ትበላለች ፡ ደምም ፡ ታፈስላቸዋለች ፡ ከወይ
ኑም ፡ ፍልቅ ፡ አድርጋ ፡ ትጠጣለች ፡ ዕጣን ፡
ታጥንላቸዋለች፡የዕጣኑንም፡መዓዛ፡ታሸትት
ላቸዋለች፡ጣዖቶቿ፡ያገዟታል፡እሷም፡ትታ
ዘገዛላቸዋለች ።
ዳግመኛም ፡ ሴት ፡ ልጆቿን ፡ ወንዶች ፡ ልጆ ፳፩፤
ቿን ፡ ትሠዋላቸዋለች ፡ ስለ ፡ ፍቅራቸውም ፡
ምስጋና፡ታቀርብላቸዋለችና፡ባንደበቷ፡በተ
ናገረችው፡ነገርና፡በእጆቿ፡ሥራ፡ደስ፡ይላ
ታል ።
ቍርጥ፡ፍርድ፡በሚደረግበት፡ቀን፡ለሷ፡ወዮ ፳፪፤
ላት ፡ ለምትወዳቸው ፡ ለምትዋሀዳቸው፡ለጣ
ዖቶቿም፡ወዮላቸው ፤ ትሉ ፡ ወደማያንቀላፋ
በት ፡ እሳቱ፡ወደማይጠፋበት ፡ ከለሳቸውም ፡
ጋራ ፡ ከሲኦል ፡ በታች ፡ ወዳለ ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡
ትወርዳለች ።
የፈጠርኩሽ፡እኔን፡ትተሽ፡ልዩ፡የሆኑ፡ጣዖ ፳፫፤
ቶችን፡አምልከሻልና፡የጐሰቈልሽ፡የኢየሩሳ
ሌም፡ልጅ፡ወዮልሽ ።
እኔም ፡ እንደ ፡ ሥራሽ ፡ ፍዳውን ፡ አመጣብሻ ፳፬፤

ለሁ፡ አሳዝነሽኛልና ፡ ቃሌንም ፡ ቸል ፡ ብለሽዋ
ልና ፡ በጎ ፡ ሥራንም ፡ አልሠራሽምና ፡ ወደ ፡
ተግዳሮትሽ ፡ አፈርድብሻለሁ ።
፳፭ እንቺ ፡ ቃሌን ፡ አሳዝነሽዋልና ፡ ሕጌን ፡ ትጠ
ብቂ ፡ ዘንድ ፡ እኔም ፡ ከንቺ ፡ ጋራ ፡ በረድኤት ፡
እኖር ፡ ዘንድ ፡ ከሚጣሉሽም ፡ ሁሉ ፡ አድንሽ ፡
ዘንድ ፡ አንቺም ፡ ያዘዝኩሽን ፡ ሥርዓቴንም ፡
ትጠብቂ ፡ ዘንድ ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ በተማማልሽበት ፡
ሕጌም ፡ ጸንተሽ ፡ አልኖርሽምና ፡ እኔም ፡ ቸል ፡
እልሻለሁ ፡ ፈጥኜም ፡ ከመከራው ፡ አላድንሽም ።
፳፮ ይህን ፡ ሁሉ ፡ አልጠበቅሽም ፡ እኔም ፡ ቸል ፡
አልሁሽ ፡ እኔ ፡ ፈጥሬሻለሁና ፡ ትእዛዜና ፡ ቃሌ
ንም ፡ አልጠበቅሽምና ፡ በፍርድ ፡ ጊዜ ፡ አፈርድብ
ሻለሁ ፡ የኔም ፡ ወገን ፡ ትሆኚ ፡ ዘንድ ፡ አከበርሁሽ ።
፳፯ ገሞራና ፡ ሰዶም ፡ ከኔ ፡ እንደ ፡ ተለዩ ፡ አንቺም ፡
ከኔ ፡ ተለየሽ ።
፳፰ እኔም ፡ ፈርጄ ፡ አጠፋኋቸው ፡ ሰዶምና ፡ ገሞራ ፡
ከኔ ፡ እንደ ፡ ተለዩ ፡ አንቺም ፡ ከኔ ፡ ተለየሽ ፡
አሁንም ፡ ተቈጥቼ ፡ እንዳጠፋኋቸው ፡ አን
ቺንም ፡ ተቈጥቼ ፡ አጠፋሁሽ ፡ እኔ ፡ ካጠፋኋ
ቸው ፡ ከሰዶም ፡ ከገሞራ ፡ ወገን ፡ ነሽና ፡ አጠ
ፋሁሽ ፡ ወደ ፡ ጕልማሳ ፡ ሚስት ፡ በመሔድ ፡
ከሴቶች ፡ ጋር ፡ እንደ ፡ መድረስ ፡ ከእንስሳና ፡
ከወንድ ፡ ጋራ ፡ ያለ ፡ ሕግም ፡ በመስሰን ፡ የፈ
ጠርኋቸው ፡ እኔን ፡ አሳዝነውኛልና ፡ በተድላ ፡
በደስታቸው ፡ እንዳይኖሩ ፡ ስም ፡ አጠራራቸ
ውን ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ አጠፋሁ ።
፳፱ ከሕፃን ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ሽማግሌ ፡ ድረስ ፡ በፊ
ታቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ የለም ፡
በክፉ ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ይረዳቃል ፡ እንጂ ፡ እሺን ፡
መሥራት ፡ ይተዉ ፡ ዘንድ ፡ አንዱ ፡ አንዱን ፡
አይቈጣውም ፡ ሥራቸው ፡ ክፉ ፡ ነውና ፡ ኃጢ
አትንና ፡ በደልን ፡ የጠገቡ ፡ ናቸው ።
፴ ክፉ ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ቅሚያና ፡ ትዕቢት ፡ ስስትም ፡
በልቡናቸው ፡ የተዘጋጀ ፡ ነው ።
፴፩ ስለዚህም ፡ ነገር ፡ እግዚአብሔር ፡ ቸል ፡ አላ
ቸው ፡ አገሮቻቸውንም ፡ አጠፋቸው ፡ ሥር ፡
መሠረታቸው ፡ እስኪጠፋ ፡ ድረስ ፡ በእሳት ፡
ያቃጠላቸውም ፡ አሉ ፡ እስከ ፡ ዘለዓለሙ ፡
ድረስ ፡ ፈጽመው ፡ ጠፉ ፡ እንጂ ፡ ከነርሳቸው ፡
አንድ ፡ ስንኳ ፡ አላስቀረም ።
፴፪ በኃጢአት ፡ ጸንተዋልና ፡ ቊርጥ ፡ ፍርድ ፡ እስ
ከሚደረግበት ፡ እስከ ፡ ዕለተ ፡ ምጽአት ፡ ድረስ ፡
ለዘለዓለሙ ፡ በጥፋት ፡ ይቈያሉ ፡ በክፉ ፡ ሥራ
ቸው ፡ አሳዝነውኛልና ፡ እኔም ፡ አልምራቸ
ውም ፡ ይቅር ፡ አልላቸውም ።
፴፫ እኔም ፡ ቸል ፡ አልኋቸው ፡ ሥራሽ ፡ ሁሉ ፡ ቅይ
ሚያና ፡ ኃጢአት ፡ ዝሙትና ፡ ስስት ፡ ሐሰት ፡
መናገርም ፡ የስሕተት ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ እኔም ፡
የማልወደው ፡ መሰናክል ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ተቈጥቼ ፡
በያዝኩሽ ፡ ጊዜ ፡ ምክንያት ፡ አታገኚምና ፡ የጕ
ስቈልሽ ፡ አንቺም ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ልጅ ፡ እን
ደነሳቸው ፡ ፍርድ ፡ በሚደረግበት ፡ ቀን ፡ በፍ
ርድ ፡ ትያገርለሽ ።

እኔ ፡ ለክብር ፡ አድርጌሽ ፡ ነበር ፡ አንቺ ፡ ግን ፡ ፴፬
ራስሽን ፡ አዋረድሽ ፡ እኔ ፡ የኔ ፡ ገንዘብ ፡ ብየሽ ፡
ነበር ፡ አንቺ ፡ ግን ፡ ለሌላ ፡ ሆንሽ ።
እኔ ፡ ለክብር ፡ አጭቼሽ ፡ ነበር ፡ አንቺ ፡ ግን ፡ ፴፭
ለዲያብሎስ ፡ ሆንሽ ፡ እኔም ፡ እንደ ፡ ክፉ ፡
ሥራሽ ፡ ተበቅዬ ፡ አጠፋሻለሁ ።
ቃሌን ፡ ሁሉ ፡ ስላልሰማሽ ፡ በወደድሁሽም ፡ ፴፮
ጊዜ ፡ ያዘዝሁሽን ፡ ትእዛዝ ፡ ስላልጠበቅሽ ፡ የፈ
ጠርሁሽ ፡ እግዚአብሔር ፡ እኔ ፡ ነኝና ፡ ጽኑ ፡
በቀልን ፡ አብዝቼ ፡ አመጣብሻለሁ ፡ እንዳንቺ ፡
ባሉ ፡ በኃጥአንም ፡ ሁሉ ፡ አፈርዳለሁ ፡ እንደ ፡
ክፉ ፡ ሥራቸውም ፡ ፍርድ ፡ በሚፈረድበት ፡
ቀን ፡ ፍዳውን ፡ አመጣባቸዋለሁ ።
ቃሌን ፡ አልጠበቅሽምና ፡ ፍርዴንም ፡ ቸል ፡ ፴፯
ብለሻልና ፡ ከነርሱ ፡ ጋራ ፡ አፈርድብሻለሁ ።
በልቡናችሁ ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ ፴፰
የሌለባችሁ ፡ ገሞራና ፡ ሰዶም ፡ ወዮላችሁ ።
በእሳተ ፡ ገሃነም ፡ ከንቺ ፡ ጋራ ፡ በአንድነት ፡ የሚ ፴፱
ፈረድባት ፡ እኅትሽ ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ልጅ ፡ እን
ደዚሁ ፡ ሁሉ ፡ ወዮላት ፡ ለዘለዓለሙ ፡ መውጫ ፡
ወደሌለበት ፡ ወደ ፡ ተዘጋጀላችሁ ፡ ወደ ፡ ገሃ
ነም ፡ አንድነት ፡ ትወርዳላችሁና ፡ ያንቺንም ፡
ኃጢአት ፡ የሠሩ ፡ ኃጢአተኞች ፡ ሁሉ ፡ ወዮ
ላቸው ።
ትእዛዜንና ፡ ቃሌን ፡ አልጠበቃችሁምና ፡ ትእ ፵
ዛዜንና ፡ ቃሌን ፡ ያልጠበቃችሁ ፡ አንቺና ፡ እርሷ ፡
ፍርድ ፡ በሚፈረድበት ፡ ቀን ፡ በአንድነት ፡ ወደ ፡
ሲኦል ፡ ትወርዳላችሁ ።
ትእዛዜንና ፡ ቃሌን ፡ የጠበቁ ፡ ደጋጎች ፡ ሰዎች ፡ ፵፩
ግን ፡ ኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ ያደለቡትን ፡ ገን
ዘብ ፡ ይበላሉ ፡ ክፉዎች ፡ ሰዎች ፡ የማረኩት
ንም ፡ ምርኮ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘ ፡ ደጋ
ጎች ፡ ሰዎች ፡ ይከፈላሉ ፡ ደጋጎች ፡ ሰዎችም ፡
ፈጽመው ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
በደለኞችና ፡ ኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ያለ ፵፪
ቅሳሉ ፡ ከትእዛዜ ፡ ወጥተው ፡ ስለ ፡ በደሉት ፡
ኃጢአታቸውም ፡ ሁሉ ፡ ያዝናሉ ።
ቃሌን ፡ የሚጠብቅ ፡ በትእዛዜም ፡ ጸንቶ ፡ የሚ ፵፫
ኖር ፡ በረከቴን ፡ የሚያገኝ ፡ በኔ ፡ ዘንድ ፡ የሚ
ከብር ፡ እርሱ ፡ ነው ።
ቃሌን ፡ የሚጠብቅ ፡ በትእዛዜም ፡ ጸንቶ ፡ የሚ ፵፬
ኖር ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ከምድር ፡ የተገኘውን ፡
ድልብ ፡ ይበላል ፡ ቅን ፡ ልቡና ፡ ያላቸው ፡ ደጋ
ጎች ፡ ነገሥታት ፡ ወደ ፡ ገቡበት ፡ ወደ ፡ ገነትም ፡
ገብቶ ፡ ይኖራል ።

ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

በያዝኋቸው ፡ ጊዜ ፡ በመዓቴ ፡ ይጐስቊላ ፩
ሉና ፡ ይጠፋሉና ፡ ዛሬ ፡ ራሳቸውን ፡ ለሚያስታ
ብዩ ፡ ለጢሮስና ፡ ለሲዶና ፡ ለይሁዳ ፡ አገር ፡
አውራጃዎች ፡ ሁሉ ፡ ወዮላቸው ።
እሽናፊ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡ ፈጽሞ ፡ ፪
ትዕቢተኛ ፡ የሚሆን ፡ የዲያብሎስ ፡ ልጅ ፡ ለሐሰ
ትት ፡ ነገር ፡ ጠላቷ ፡ የሚሆን ፡ ክፋደ ፡ ልቡና

ውን ፡ የሚያጸና ፡ የሚመክ ፡ ፈጣሪውን ፡ የማ
ያውቅ ፡ ሐሳዊ ፡ መሲሕ ፡ ከነሱ ፡ ይወለዳል ፡
ብሏልና ፡ ወዮላቸው ፡ አለ ፡ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡
እግዚአብሔርም ፡ በሱ ፡ ኃይሉን ፡ እገልጽ ፡
ዘንድ ፡ ለቍጣዬ ፡ አምሳል ፡ አደረግሁት ፡ አለ።
፫፤ ይቺም ፡ ቅፍርናሆም ፡ ሰማርያና ፡ ገሊላ ፡ ደማ
ስቆና ፡ ሶርያም ፡ አክያና ፡ ቆጵሮስም ፡ የዮርዳ
ኖስም ፡ አውራጃ ፡ ሁሉ ፡ ክፉደ ፡ ልቡናቸውን ፡
ያጸኑ ፡ በኃጢአታቸው ፡ ጸንተው ፡ የሚኖሩ ፡
የሞት ፡ ጥላና ፡ ጨለማም ፡ የሸፈናቸው ፡ ወገ
ኖች ፡ ናቸው ፡ ዲያብሎስ ፡ ልቡናቸውን ፡ በኃ
ጢአት ፡ ሸፍኖታልና ፡ ለዚያም ፡ ለትዕቢተኛ ፡
ለዲያብሎስ ፡ ይታዘዙለታልና ፡ እግዚአብሔር
ንም ፡ ወደ ፡ መፍራት ፡ አይመለሱም ።
፬፤ ለአጋንንት ፡ የሚታዘዙላቸው ፡ በስማቸውም ፡
መሥዋዕት ፡ የሚሠዉላቸው ፡ ሰዎች ፡ የዚያን ፡
ጊዜ ፡ ወዮላቸው ፡ የፈጠራቸው ፡ እግዚአብ
ሔርን ፡ ክደውታልና ፡ አእምሮ ፡ የሌላቸው ፡
እንስሳትን ፡ ይመስላሉ ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ሕግ ፡ የዘነጋ ፡ የዲያብሎስ ፡ ልጅ ፡ የሚሆን ፡
ሐሳዊ ፡ መሲሕ ፡ በበታው ፡ ሁሉ ፡ ምስሉን ፡ ያቆ
ማልና ፡ (አምላክ ፡ ነኝ ፡ ብሏልና ፡) በልቡናው ፡
ፈቃድና ፡ በእጁ ፡ ሥራ ፡ በቅሚያና ፡ በኃጢአ
ቱም ፡ ሁሉ ፡ በክዳትና ፡ በበደልም ፡ በቅሚ
ያና ፡ ሰው ፡ በሚሠራው ፡ ዝሙት ፡ ሁሉ ፡ በሐ
ሰት ፡ ነገርም ፡ ደስ ፡ ይለዋል ።
፭፤ ይህንን ፡ እንዲሠራ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡
የተቈጠረ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ኃጢአት ፡ እንዲሠሩ ፡
ዘመኑ ፡ ይታወቃልና ።
፮፤ ፀሐይ ፡ ትጨልማለች ፡ ጨረቃም ፡ ደም ፡ ትሆ
ናለች ፡ ከዋክብትም ፡ ከሰማይ ፡ ይረግፋሉ ፡ ምድ
ርን ፡ ያሳልፋት ፡ ዘንድ ፡ በውስጧም ፡ በሚኖሩ ፡
ሰዎች ፡ ኃጢአት ፡ የሚኖረውን ፡ ሁሉ ፡ ያሳል
ፈው ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ በፍጻሜ ፡ ዘመን ፡
በሚያመጣው ፡ ተአምራት ፡ ሥራው ፡ ሁሉ ፡
ያልፋል ።
፯፤ እግዚአብሔር ፡ በፈጠረው ፡ ፍጥረት ፡ ላይ ፡ ከር
ቷልና ፡ ፈጥኖም ፡ የወደደውን ፡ ሁሉ ፡ ባንድ ፡
ሰዓት ፡ አድርጓልና ፡ ታናሽ ፡ ጠላት ፡ ዲያብሎ
ስን ፡ የጊታ ፡ ሞት ፡ ያጠፋዋል ።
፰፤ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ እግዚአብሔር ፡ እኔ ፡ ፈርጁ ፡
አጠፋለሁ ፡ ብሏልና ፡ ከምጽአት ፡ በኋላ ፡ ግን ፡
ለዲያብሎስ ፡ ሥልጣን ፡ የለውም ።
፱፤ እሱም ፡ በቍጣዬ ፡ በተያዘበት ፡ ቀን ፡ ደጅ ፡ የሚ
ጠናላት ፡ ጽኑ ፡ መከራ ፡ ወዳላት ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡
ይወርዳል ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ ያሉትን ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡
መቅሠፍትና ፡ ወደ ፡ ጥፋት ፡ ወደ ፡ ክህደትም ፡
ይወስዳልና ፡ ከገሃነም ፡ የማወጣ ፡ ወደ ፡ ገሃነ
ምም ፡ የማገባ ፡ እኔ ፡ ስለ ፡ ሆንኩ ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡
ይወርዳል ።
፲፤ እሱ ፡ ለደከሙ ፡ ሰዎች ፡ ጽናትና ፡ ኃይልን ፡ ይሰ
ጣልና ፡ ዳግመኛም ፡ ለኃይለኞችና ፡ ለፅኑ ፡
ሰዎች ፡ ድካምን ፡ ይሰጣልና ፡ ኃይለኛ ፡ በኃ
ይሉ ፡ አይመክ ።

እሱ ፡ ገዥ ፡ ነውና ፡ የሚበደሉትንም ፡ ሰዎች ፡ ፲፩፤
ከሚበድሏቸው ፡ ሰዎች ፡ እጅ ፡ ፈርዶ ፡ ያድና
ቸዋልና ፡ የበልቴቶችና ፡ አበት ፡ እናቱ ፡ የሞቱ
በትን ፡ ልጅ ፡ በቀል ፡ ይመልሳል ።
ለምትመኪ ፡ ክፋደ ፡ ልቡናሽንም ፡ ለምታጸኚ ፡ ፲፪፤
የማልገዛሽ ፡ ፈርጄም ፡ የማላጠፋሽ ፡ ለሚመስ
ልሽ ፡ ላንቺ ፡ ወዮልሽ ፡ በመመኪቱና ፡ በትዕ
ቢቱ ፡ ዙፋኔን ፡ በከዋክብትና ፡ በሰማይ ፡ ላይ ፡
እዘረጋለሁ ፡ ከፍ ፡ እንዳለ ፡ እንደ ፡ እግዚአብ
ሔርም ፡ እሆናለሁ ፡ ብሏልና ።
ከሁሉ ፡ አስቀድሞ ፡ የተፈጠረ ፡ እንደ ፡ አጥ ፲፫፤
ቢያ ፡ ኮከብ ፡ የሚያበራ ፡ ዲያብሎስ ፡ ከሰማይ ፡
እንዴት ፡ ወረደ ፡ ብሎ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ ላን
ቺም ፡ ወዮልሽ ።
ይኸንንም ፡ በትዕቢትህ ፡ ደፍረህ ፡ ተናገርህ ፡ ፲፬፤
ፈጽሞ ፡ በሥልጣኑ ፡ የፈጠረህ ፡ እግዚአብሔ
ርንም ፡ አላሰብኸውም ፡ በልቡናህ ፡ ጽናት ፡ ወደ ፡
ገሃነም ፡ ትወርድ ፡ አንተ ፡ ራስክን ፡ ለምን ፡ አከ
ራህ ።
ከእሳት ፡ ከነፋስ ፡ የፈጠራቸው ፡ እሱ ፡ እንደ ፡ ፲፭፤
ሆነ ፡ ስላወቁ ፡ እነሳቸው ፡ በተዋረደ ፡ ልቡና ፡
ፈጣሪያቸውን ፡ ያመሰግኑታልና ፡ ከትእዛዙም ፡
አይወጡምና ፡ ከትእዛዙም ፡ ፈጽመው ፡ እንዳ
ይወጡ ፡ ልቡናቸውንም ፡ ከክህደት ፡ ይጠብቃ
ሉና ፡ እንዳንተ ፡ ካሉ ፡ ከመላእክት ፡ ሁሉ ፡ ተለ
ይተህ ፡ ተዋረድህ ።
አንተ ፡ ግን ፡ በልቡናህ ፡ ትዕቢት ፡ ጽኑ ፡ ክህደ ፲፮፤
ትን ፡ አደረግህ ፡ ካንተ ፡ ወገን ፡ የሚሆኑ ፡ እን
ዳንተም ፡ የሚወነጅሉ ፡ ኃጢአትን ፡ በምታስ
ተምርበት ፡ በትእዛዝህና ፡ በፈቃድህም ፡ ሁሉ ፡
ጸንተው ፡ የሚኖሩ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡
የዘነጉ ፡ ሰዎችና ፡ እንዳንተ ፡ ያሉ ፡ ኃጢአተ
ኞች ፡ ጸንተው ፡ የሚኖሩበት ፡ ኃጢአትንና ፡
በደልን ፡ ቅሚያንና ፡ ክህደትን ፡ ሁሉ ፡ አንተ ፡
ትከበክበዋለህና ፡ ከባልንጀሮችህ ፡ ተለይተህ ፡
የጐሰቈለ ፡ ሰውን ፡ ሆንህ ።
በተንኰልህ ፡ ያሳትካቸው ፡ አጋንንትና ፡ አንተ ፡ ፲፯፤
አንድነት ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡ ትወርዳላችሁና ፡ ወዮ
ልህ ።
በሚያስት ፡ በዚያ ፡ በወንጀለኛ ፡ በዲያብሎስ ፡ ፲፰፤
የሳታችሁ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፡
ወዮላችሁ ፡ እሱ ፡ በስተማራችሁ ፡ ሠራዊቱም ፡
በስተማሯችሁ ፡ ገንዘብ ፡ እንደሱ ፡ ስታችኋልና ፡
ለዘለዓለም ፡ መውጫ ፡ ወደሌለበት ፡ ወደ ፡ ገሃ
ነም ፡ በንድነት ፡ ትወርዳላችሁ ።
ቀድሞም ፡ የእግዚአብሔር ፡ በሪያ ፡ ሙሴ ፡ ሳለ ፡ ፲፱፤
ክርክር ፡ በተደረገበት ፡ ውኃና ፡ በኮሬብ ፡ በአ
ማሌቅና ፡ በደብረ ፡ ሲናም ፡ እግዚአብሔርን ፡
አሳዘናችሁት ።
ዳግመኛም ፡ ወደ ፡ ከነዓን ፡ ጉብኛ ፡ በላካችሁ ፡ ፳፤
ጊዜ ፡ ጐዳናው ፡ ሩቅ ፡ ነው ፡ እስከ ፡ ሰማይ ፡
የሚደርስ ፡ ቅጽራቸውም ፡ አምባቸውም ፡ ጽኑ ፡
ነው ፡ አርበኞችም ፡ በዚያ ፡ ይኖራሉ ፡ ብለው ፡
ይህንን ፡ በነገሩዋችሁ ፡ ጊዜ ፡ የሚያስጨንቅ ፡

ሥራ ፡ ወደምትሠሩበት ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ አገር ፡
ትመለሱ ፡ ዘንድ ፡ ተቈጥታችሁ ፡ የእግዚአብሔ
ርን ፡ ቃል ፡ አሳዘናችሁ ።
፳፩ ከመከራው ፡ ያዳናችሁን ፡ በግብጽም ፡ ታላላቅ ፡
ታምራት ፡ ያደረገ ፡ በመልእክትም ፡ ሥልጣን ፡
የመራችሁን ፡ እግዚአብሔርን ፡ አላሰባችሁ
ትም ። በሐይ ፡ እንዳያቃጥላችሁ ፡ ቀን ፡ በደ
መና ፡ ይጋርዳችሁ ፡ ነበር ፡ እግሬችሁም ፡ በጨ
ለማ ፡ እንዳይሰነከል ፡ ዓምደ ፡ እሳት ፡ ሌሊት ፡
ያበራላችሁ ፡ ነበር ።
፳፪ ሠራዊቱና ፡ ፈርዖንም ፡ በከፈሩዋችሁ ፡ ጊዜ ፡
ፈጽማችሁ ፡ ወደ ፡ ሙሴ ፡ ጮኻችሁ ፡ ሙሴም ፡
ፈጽሞ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኸ ፡ ከፈርዖ
ንም ፡ ጋራ ፡ እንዳትገናኙ ፡ በመልአኩ ፡ አድሮ ፡
ጠበቃችሁ ።
፳፫ እነሳቸውን ፡ ግን ፡ በመከራ ፡ ወደ ፡ ኤርትራ ፡
አገባቸው ፡ እግዚአብሔር ፡ እስራኤልን ፡ ብቻ
ውን ፡ መራቸው ፡ ከነሱም ፡ ጋራ ፡ ልዩ ፡ ጣዖት ፡
አልነበረም ፡ ብሷልና ፡ ጠላቶቻቸውን ፡ ግን ፡
አንድ ፡ ጊዜ ፡ በባሕር ፡ ቀበራቸው ፡ ከነሳቸ
ውም ፡ የሚሸሸውን ፡ አላስቀረም ።
፳፬ እስራኤልንም ፡ በባሕሩ ፡ መካከል ፡ በእግር ፡
አሻገራቸው ፡ ከግብፃውያን ፡ የተነሣ ፡ ምንምን ፡
ያገኛቸው ፡ መከራ ፡ የለም ፡ ወደ ፡ ደብረ ፡ ሲና ፡
አደረሳቸው ፡ በዚያም ፡ አርባ ፡ ዘመን ፡ መና
ውን ፡ መገባቸው ።
፳፭ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እግዚአብሔርን ፡ ሁለ
ጊዜ ፡ ያሳዝኑታልና ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ በጎ ፡ ነገር ፡
አድርጎላቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ማምለክ ፡
ቸል ፡ አሉ ።
፳፮ ከልጅነታቸው ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ያረጁ ፡ ድረስ ፡
ክፋትን ፡ በልቡናቸው ፡ አኖሩ ፡ የእግዚአብ
ሔር ፡ እፉ ፡ የአበው ፡ ልደት ፡ በተጻፈበት ፡ በኦ
ሪት ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናግሯልና ፡ የአዳም ፡
ልጆች ፡ ልቡናቸው ፡ አመድ ፡ ነው ፡ ሥራቸ
ውም ፡ ሁሉ ፡ ወደቅሚያ ፡ ነው ፡ ወደ ፡ ክፋ
ትም ፡ ይሮጣሉ ፡ በግፍ ፡ የሰውን ፡ ገንዘብ ፡ ከመ
ሰብሰብ ፡ በሐሰትም ፡ ከመማል ፡ በልንጀራንም ፡
ከመበደል ፡ ከመቀማትና ፡ ከመሥረቅ ፡ በቀር ፡
ከነሳቸው ፡ የቀናች ፡ ሥራን ፡ የሚወዳት ፡ የለም ፡
ብሎ ፡ ተናግሯልና ፡ ክፋትን ፡ በልቡናቸው ፡
አኖሩ ።
፳፯ ሁሉም ፡ በሕይወት ፡ በሚኖሩበት ፡ ዘመን ፡
ወደ ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ ይሄዳሉ ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ሕግ ፡ ያፈረሱ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ከጥንት ፡
ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ፍጻሜ ፡ ዘመን ፡ ድረስ ፡ እግዚ
አብሔርን ፡ ፈጽመው ፡ አሳዘኑት ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

፩ እግዚአብሔርም ፡ የቀደመ ፡ ወገኖች ፡ የቃየ
ንን ፡ ልጆች ፡ ስለ ፡ ኃጢአታቸው ፡ በጥፋት ፡
ውኃ ፡ በጠፉቸው ፡ ጊዜ ፡ ምድርን ፡ በማየ ፡
አይኅ ፡ አጠመቃት ፡ ከቃየል ፡ ልጆችም ፡ ኃጢ
አት ፡ ሁሉ ፡ አነፃት ።
ሰውን ፡ ስለ ፡ ፈጠርሁት ፡ አዘንሁ ፡ ብሏልና ፡ ፪
በደለኞችን ፡ ሁሉ ፡ አጠፋ ፡ ከስምንት ፡ ሰዎች ፡
በቀር ፡ አላስቀረም ፡ ሁሉን ፡ አጠፋ ፡ ከዚህ ፡
በኋላ ፡ እነሱን ፡ አበዛቸው ፡ ምድርንም ፡ መዓት ፡
ያበቃቸው ፡ የአዳምን ፡ ርስት ፡ ተከፈሉ ።
ኖኅ ፡ ግን ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጋራ ፡ ተማማለ ፡ ፫
መሐላን ፤ እግዚአብሔር ፡ ምድርን ፡ ዳግመኛ ፡
በጥፋት ፡ ውሀ ፡ እንዳያጠፋት ፡ የኖኅም ፡ ልጆች ፡
የበኩተውንና ፡ ሙቶ ፡ ያደረውን ፡ እንዳይበሉ ፡
ከፈጠራቸው ፡ ከእግዚአብሔር ፡ በቀር ፡ ልዩ ፡
የሆኑ ፡ ጣዖቶችን ፡ እንዳያመልኩ ፡ እርሱም ፡
የፍቅር ፡ አባት ፡ ይሆናቸው ፡ ዘንድ ፡ በከንቱ ፡
ኃጢአታቸውም ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ እንዳያጠፋ
ቸው ፡ የሰተኑንና ፡ የበልጉንም ፡ ዝናም ፡ እንዳ
ይከለክላቸው ፡ ሰኩብትና ፡ ለሰዎች ፡ በየጊዜ
ውም ፡ ምግባቸውን ፡ ይሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ ማሩ
ንና ፡ የእህሉን ፡ ፍሬ ፡ ተክልንም ፡ ይሰጣቸው ፡
ዘንድ ፡ እነርሳቸውም ፡ እግዚአብሔር ፡ በሚ
ወደው ፡ ሁሉ ፡ በጎ ፡ ሥራን ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡
ከእግዚአብሔር ፡ ጋራ ፡ መሐላን ፡ ተማማሉ ።
ይኸንንም ፡ ሥርዓት ፡ ከሰጣቸው ፡ በኋላ ፡ የእስ ፬
ራኤል ፡ ልጆች ፡ በኃጢአታቸው ፡ እግዚአብሔ
ርን ፡ አሳዘኑት ፡ የፈጣሪያቸውን ፡ የእግዚአብ
ሔርን ፡ ሕግ ፡ እንዳላፈረሱ ፡ እንዳባቶቻቸው ፡
እንደ ፡ ይስሐቅና ፡ እንደ ፡ አብርሃም ፡ እንደ ፡
ያዕቆብም ፡ በሕጉ ፡ ጸንተው ፡ አልኖሩም ።
ከታናናሾቹም ፡ ጀምረው ፡ እስከ ፡ ታላላቆቹ ፡ ፭
ድረስ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕጉን ፡ ያልጠበቁ ፡
እነዚያ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በሥራቸው ፡
ጠማሞች ፡ ናቸው ።
ካህናቶቻቸውም ፡ አለቆቻቸውም ፡ ጸሐፊዎቻቸ ፮
ውም ፡ ቢሆኑ ፡ ሁሉም ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ሕጊ ፡ ያፈርሳሉ ።
በፍጹም ፡ ሰውነትህና ፡ በፍጹም ፡ ልቡናህ ፡ ፯
ፈጣሪህ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ውደደው ፡ ብሎ ፡
በዳግም ፡ ሕግ ፡ ሙሴ ፡ ባዘዛቸው ፡ በእግዚአ
ብሔር ፡ ሥርዓትና ፡ ሕጉ ፡ ጸንተው ፡ አይኖሩም ።
ባልንጀራህን ፡ እንደ ፡ ሰውነትህ ፡ ውደድ ፡ ልዩ ፡ ፰
የሆኑ ፡ ጣዖቶቹንም ፡ አታምልክ ፡ ወደጉል
ማሳ ፡ ሚስትም ፡ አትሂድ ፡ ነፍስ ፡ አትግደል ፡
አትስረቅ ።
በሐሰትም ፡ አትመስክር ፡ አህያውም ፡ ቢሆን ፡ ፱
በሬውም ፡ ቢሆን ፡ የባልንጀራህን ፡ ገንዘብ ፡
ወንድምህ ፡ የገዛውንም ፡ ሁሉ ፡ አትውደድ ፡
ብሎ ፡ ሕግ ፡ በተጻፈበት ፡ መጽሐፍ ፡ ሙሴ ፡ በዘ
ዛቸው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ሥርዓትና ፡ በሕጉ ፡
አይጸኑም ።
ነገር ፡ ግን ፡ ይኸን ፡ ሁሉ ፡ ካዘዛቸው ፡ በኋላ ፡ ፲
ክፉዎች ፡ የሆኑ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡
ክዳትና ፡ ወደ ፡ ኃጢአት ፡ ወደ ፡ ቅሚያና ፡
ወደ ፡ በደል ፡ ወደ ፡ ጉልማሳ ፡ ሚስት ፡ ወደ ፡
ሐሰትና ፡ ወደ ፡ መስረቅም ፡ ጣዖቶችንም ፡
ወደማምለክ ፡ ይመለሳሉ ።
ወደ ፡ ማር ፡ የሚሠማራ ፡ ላምን ፡ በመሥራት ፡ ፲፩

የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በኮሬብ ፡ እግዚአብሔ
ርን ፡ አሳዘኑት ፡ እነሆ ፡ ከግብፅ ፡ ያወጡን ፡
ፈጣሪዎቻችን፡እነዚህ፡ናቸው፡ብለው፡ሰገዱ።
፲፪፤ በኛቸውም ፡ ሥራ ፡ ደስ ፡ አላቸው ፡ በልተው ፡
ጠጥተውም ፡ ቢጠግቡ ፡ ሊዘፍኑ ፡ ተነሡ ።
፲፫፤ እግዚአብሔር ፡ አገዛዝ ፡ ከለበት ፡ ከግብፅ ፡
አገር ፡ ያወጣሀቸው ፡ ወገኖችህ ፡ ከሕግ ፡ ወጥ
ተው ፡ በደሉ ፡ የላም ፡ ምስልም ፡ ሠርተው ፡
ለጣዖቱ ፡ ሰገዱ ፡ ብሎ፡ታልና ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡
ሙሴ ፡ ተቈጥቶ ፡ ከሲና ፡ ተራራ ፡ ወረደ ።
፲፬፤ ሙሴ ፡ ወገኖቹን ፡ እየተቈጣቸው ፡ ከባለሟሉ ፡
ከኢያሱ ፡ ጋራ ፡ ወረደ ፡ ኢያሱም ፡ በሰማ ፡
ጊዜ ፡ እነሆ ፡ በእስራኤል ፡ ሰፈር ፡ ያርበኞች ፡
ድምፅ ፡ እሰማለሁ ፡ አለ ።
፲፭፤ ሙሴም ፡ ኢያሱን ፡ እስራኤል ፡ ያልፈላውን ፡
ጠጅ ፡ ጠጥተው ፡ ሲጫወቱ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ያር
በኞስ ፡ ድምጽ ፡ አይደለም ፡ አለው ፡ ወርዶም ፡
ምስላቸውን ፡ ሰበረው ፡ እንደ ፡ ትቢያም ፡ እስ
ኪሆን ፡ ድረስ ፡ ፈጽሞ ፡ አደቀቀው ፡ የእስራ
ኤል ፡ ልጆች ፡ በተራራው ፡ አጠገብ ፡ በሚጠ
ጡት ፡ ውኃ ፡ ውስጥ ፡ በጠበጠው ።
፲፮፤ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ስለ ፡
ሠሩት ፡ ኃጢአት ፡ ከህናቱን ፡ እርስ ፡ በሳቸው ፡
ይጋደሉ ፡ ዘንድ ፡ አዘዛቸው ።
፲፯፤ እነሳቸውን ፡ ከመግደል ፡ አባቶቻቸውንም ፡
ከመግደል ፡ እግዚአብሔርን ፡ መገዳደር ፡ እን
ዲበልጥ ፡ አውቀው ፡ እንዳዘዛቸው ፡ አደረጉ ።
፲፰፤ ሙሴም ፡ የመገባችሁን ፡ የተከባከባችሁን ፡ ከአ
ገዛዝም ፡ ቤት ፡ ያወጣችሁን ፡ ለነሳቸው ፡ ከነሳ
ቸው ፡ በኋላ ፡ ለልጆቻቸው ፡ ይሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡
ላባቶቻችሁ ፡ የማለላቸው ፡ ርስትንም ፡ ያወረ
ሳችሁ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ስላሳዘናችሁት ፡ ስለ
ዚህ ፡ ነገር ፡ እግዚአብሔርን ፡ ደስ ፡ አሰኛች
ሁት ፡ አላቸው ።
፲፱፤ ወደ ፡ ኃጢአትና ፡ ወደ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ይሄዳሉና ፡
በዚያም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ማሳዘን ፡ አልተ
ዉም ።
፳፤ ከሕፃንነታቸው ፡ ጀምረው ፡ እስከ ፡ ጕልማስነታ
ቸው ፡ እስከ ፡ እርጅናቸውም ፡ ድረስ ፡ በምድር ፡
ላይ ፡ ያለውን ፡ በሰማይም ፡ ለሚወዱት ፡ ሰዎች ፡
ያዘጋጀውን ፡ ይሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ በበጎ ፡ ሥራ
ቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ደስ ፡ እንዳሰኙት ፡ እን
ዳባቶቻቸው ፡ እንደ ፡ ይስሐቅና ፡ እንደ ፡ አብር
ሃም ፡ እንደ ፡ ያዕቆብም ፡ አይደሉም ፡ በዚህ ፡
ዓለም ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ የሚገኝበት ፡ ምድረ ፡
ርስትን ፡ በወዲያውም ፡ ዓለም ፡ ለደጋግ ፡ ሰዎች ፡
የተዘጋጀች ፡ ደስ ፡ የምታሰኝ ፡ ገነትን ፡ ዓይን ፡
ያላየውን ፡ ጆሮም ፡ ያልሰማውን ፡ በሰው ፡ ልቡ
ናም ፡ ያልታሰበውን ፡ እግዚአብሔርን ፡ በሕይ
ወት ፡ ሳሉ ፡ ደስ ፡ ላሰኙት ፡ ለሚወዱት ፡ ለአ
ብርሃም ፡ ለይስሐቅ ፡ ለያዕቆብ ፡ ያዘጋጀውን ፡
ይሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ በሥራቸው ፡ ደስ ፡ እንዳ
ሰኙት ፡ እንደ ፡ አብርሃም ፡ እንደ ፡ ይስሐቅ ፡
እንደ ፡ ያዕቆብ ፡ አይደሉም ።

እግዚአብሔርን ፡ የካዱ ፡ ክፉዎችም ፡ የሆኑ ፡ ፳፩፤
በልቡናቸው ፡ ፈቃድ ፡ ጸንተው ፡ የሚኖሩ ፡
የነሳቸው ፡ ልጆችም ፡ የመገባቸውን ፡ የተከባ
ከባቸውን ፡ ከሕፃንነታቸውም ፡ ጀምሮ ፡ የጠበ
ቃቸውን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ አልሰ
ሙም ።
ከግብፅ ፡ ምድር ፡ ያወጣቸውን ፡ ከጡብ ፡ ሥራ ፡ ፳፪፤
ከጽኑም ፡ አገዛዝ ፡ ያዳናቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡
አላሰቡትም ።
እነሳቸው ፡ ግን ፡ ፈጽመው ፡ አሳዘኑት ፡ እሱም ፡ ፳፫፤
በዙሪያቸው ፡ ያሉ ፡ አሕዛብን ፡ ያስነሣባቸው ፡
ነበር ፡ እነሳቸውም ፡ በጠላትነት ፡ ተነሥተውብ
ቸው ፡ እንደ ፡ ወደዱም ፡ ያስገብሯቸው ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

የዚያን ፡ ጊዜም ፡ የምድያም ፡ ሰዎች ፡ በጠ ፩፤
ላትነት ፡ ተነሡባቸው ፡ እስራኤልንም ፡ ይወጓ
ቸው ፡ ዘንድ ፡ ሠራዊቶቻቸውን ፡ አስነሡባቸው ፡
የንጉሣቸውም ፡ ስሙ ፡ አክራንድስ ፡ ይባላል ፡
በኪልቅያና ፡ በሶርያ ፡ በደማስቆም ፡ ያሉ ፡ ብዙ ፡
ሠራዊትን ፡ ፈጥኖ ፡ ሰበሰበ ።
በዮርዳኖስም ፡ ማዶ ፡ ሰፍሮ ፡ ገንዘባችሁንም ፡ ፪፤
እማርክ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ግብር ፡ ገብ
ሩልኝ ፡ ብሎ ፡ መልክተኞች ፡ ላከ ፡ ባትገብሩኝ ፡
ግን ፡ እናንተን ፡ እቀጣችሁ ፡ ዘንድ ፡ ከብቶቻች
ሁን ፡ እማርክ ፡ ባዝራችሁን ፡ እወስድ ፡ ልጆቻ
ችሁንም ፡ እማርክ ፡ ዘንድ ፡ መጣሁ ፡ አላቸው ።
ወደማታውቁት ፡ አገር ፡ ማርኬ ፡ እወስዳችኋ ፫፤
ለሁ ፡ በዚያም ፡ ወኃ ፡ ቀጂዎችን ፡ እንጨት ፡
ለቃሚዎችን ፡ አደርጋችኋለሁ ፡ አላቸው ።
እኛ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ወገኖች ፡ ነን ፡ የሚች ፬፤
ለንም ፡ የለም ፡ እያላችሁ ፡ አትመኩ ፡ አጠፋ
ችሁ ፡ ዘንድ ፡ ገንዘባችሁንም ፡ እዘርፍ ፡ ዘንድ ፡
እግዚአብሔር ፡ የላከኝ ፡ አይደለምን ፡ ወገናች
ሁንም ፡ ሁሉ ፡ እሰበስብ ፡ ዘንድ ፡ የላከኝ ፡ አይ
ደለሁምን ።
እኔ ፡ ያጠፋኋቸውን ፡ ሌሎች ፡ ወገኖች ፡ በውኑ ፡ ፭፤
ልዩ ፡ ጣዖቶቻቸው ፡ ያዳኗቸው ፡ ማዳን ፡ አለን ፡
በዝራቸውንና ፡ ፈረሳቸውን ፡ ማረክሁ ፡ እነሳቸ
ውንም ፡ ገደልኩ ፡ ልጆቻቸውንም ፡ ማረክሁ ።
ያዘገኳችሁን ፡ ግብር ፡ ካላገባችሁልኝ ፡ እናንተ ፮፤
ንም ፡ እንደነሳቸው ፡ አደርጋችኋለሁ ፡ አለ ፡ ከብ
ቶቻቸውንና ፡ ገንዘባቸውን ፡ ይዘርፉ ፡ ሚስቶ
ቻቸውንም ፡ ይማርክ ፡ ዘንድ ፡ ዮርዳኖስም ፡
ተሻገረ ።
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ ፯፤
እግዚአብሔር ፡ ጽኑ ፡ ልቅሶን ፡ አለቀሱ ፡ ፈጽ
መውም ፡ ጮሁ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ የሚረዳቸው ፡
አጡ ።
ስለዚህም ፡ ነገር ፡ ለሦስቱ ፡ ወንድማማቾች ፡ እግ ፰፤
ዚአብሔር ፡ ጽናትን ፡ ሰጣቸው ፡ ስማቸውም ፡
እንደዚህ ፡ ነው ፡ መልካቸውም ፡ ያማረ ፡ በኃይ
ላቸውም ፡ አርበኞች ፡ የሆኑ ፡ ይሁዳና ፡ መብክ
ዩስ ፡ መቃቢስ ፡ ናቸው ።

፱፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ፈጽመው ፡ በዚያ ፡ አለ
ቀሱ ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡
ጩኸት ፡ የተነሣ ፡ ልቡናቸውን ፡ አሳዘናቸው ፡
እናቱና ፡ አባቱ ፡ የሞቱበት ፡ ልጅና ፡ ባልቴቶች ፡
ሹማምቶቻቸውና ፡ ከህናቶቻቸውም ፡ የእስራ
ኤል ፡ ወገን ፡ ሁሉ ፡ ሴቶችና ፡ ወንዶችም ፡ ልጆ
ችም ፡ ሁሉ ፡ በራሳቸውም ፡ ላይ ፡ አመድ ፡ ነስ
ንሰው ፡ ያለቅሱ ፡ ነበር ፡ መኳንንቶቻቸውም ፡
ማቅ ፡ ለብሰው ፡ ነበር ።
፲፤ መልክ ፡ መልክም ፡ ደመ ፡ ግቡ ፡ የሆኑ ፡ እነዚያ ፡
ወንድማማቾች ፡ ግን ፡ ሒደው ፡ ያድናቸው ፡
ዘንድ ፡ ተስማሙ ፡ ሒደን ፡ ስለነዚህ ፡ ሰዎች ፡
ሰውነታችንን ፡ ለሞት ፡ እንስጥ ፡ ብለው ፡ ተማ
ከሩ ።
፲፩፤ አይዞህ ፡ አይዞህ ፡ ተባብለው ፡ በወገባቸው ፡ ሰይ
ፋቸውን ፡ ታጥቀው ፡ በእጃቸውም ፡ ጦራቸ
ውን ፡ ይዘው ፡ ሔዱ ፡ አርበኞውንም ፡ ይወነጅ
ሉት ፡ ዘንድ ፡ ተዘጋጅተው ፡ ሔዱ ።
፲፪፤ ወደ ፡ ሰፈራቸውም ፡ ደረሱ ፡ በማስደ ፡ ተቀ
ምጦ ፡ ሳለ ፡ መብክዩስ ፡ አርበኛውን ፡ (ንጉሡን ፡)
ወጋው ፡ በአፉ ፡ መብል ፡ ሳለ ፡ በአንዲት ፡ አመ
ታት ፡ አንገቱን ፡ ቈረጠው ፡ መቃብዮስና ፡ ይሁ
ዳም ፡ በንጉሡ ፡ ግራና ፡ ቀኝ ፡ ያሉ ፡ ሠራዊ
ቱን ፡ በሰይፍ ፡ መትተው ፡ ገደሉዋቸው ።
፲፫፤ ንጉሣቸውም ፡ ድል ፡ በተነሣ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ጦሮ
ቻቸው ፡ በባልንጀራቸው ፡ ልብ ፡ ገቡ ፡ ሁሉም ፡
ፈጽመው ፡ ሸሹ ፡ ቀስታቸውም ፡ ተሰበረ ፡ እነ
ርሳቸውም ፡ ድል ፡ ተነሡ ።
፲፬፤ መልክ ፡ መልክም ፡ ደመ ፡ ግቡ ፡ የሚሆኑ ፡ እነ
ዚያ ፡ ወንድማማቾች ፡ ግን ፡ ከሞት ፡ ዳኑ ፡ ምንም ፡
ምን ፡ ክፋት ፡ ነገር ፡ ያገኛቸው ፡ የለም ፡ እግዚ
አብሔር ፡ መቅሠፍትን ፡ ወደነርሳቸው ፡ መል
ሰታልና ፡ እነርሳቸው ፡ ግን ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡
ተቀራደው ፡ አለቁ ።
፲፭፤ ድል ፡ ተነሡ ፡ ሞቱ ፡ ዮርዳኖስንም ፡ ተሻገሩ ፡
እስኪሻገሩም ፡ ድረስ ፡ ገንዘባቸውን ፡ ሁሉ ፡
ጣሉ ፡ ገንዘባቸውም ፡ ሁሉ ፡ ቀረ ፡ የእስራኤ
ልም ፡ ልጆች ፡ ጠላቶቻቸው ፡ እንደሸሹ ፡ ባዩ ፡
ጊዜ ፡ ወደ ፡ ሰፈራቸው ፡ ሄደው ፡ የዘረፉትንም ፡
ገንዘባቸውንም ፡ ለራሳቸው ፡ ወሰዱ ።
፲፮፤ በወንድሞቹና ፡ በመብክዩ ፡ እጅ ፡ እግዚአብሔር ፡
እስራኤልን ፡ እንዲህ ፡ አድርጎ ፡ አዳናቸው ።
፲፯፤ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እግዚአብሔርን ፡ ደስ ፡
እያሰኙት ፡ ጥቂት ፡ ቀን ፡ ተቀመጡ ።
፲፰፤ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ዳግመኛ ፡ ወደ ፡ ኃጢአታ
ቸው ፡ ተመለሱ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እግዚ
አብሔርን ፡ በሚገባ ፡ ማምለክን ፡ ቸል ፡ አሉ ።
፲፱፤ እርሱም ፡ በማያውቋቸው ፡ የእርሻቸውን ፡ አዝ
መራ ፡ በሚሰበስቡ ፡ የወይናቸውንም ፡ በታ ፡
በሚያጠፉ ፡ መንጋቸውንም ፡ በሚዘርፉ ፡ ከብ
ቶቻቸውንም ፡ በፊታቸው ፡ አርደው ፡ በሚያ
በሏቸው ።
፳፤ ሚስቶቻቸውን ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻቸውንና ፡ ወን
ዶች ፡ ልጆቻቸውን ፡ በሚማርኩ ፡ ወገኖች ፡
እሱም ፡ ዳግመኛ ፡ ያሳዝናቸዋል ፡ ሁሉግዚ ፡
እግዚአብሔርን ፡ የሚያሳዝኑት ፡ ስለሆነ ፤ እነ
ሳቸው ፡ ሕጉን ፡ ያፈረሱ ፡ ወገኖች ፡ ናቸውና ፡
ልጆቻቸውን ፡ በፊታቸው ፡ ራስ ፡ ራሳቸውን ፡
ይቀጠቅጢቸዋል ፡ አያድናቸውም ።

ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

ይኸንን ፡ የሚያደርጉ ፡ የጢሮስና ፡ የሲዶና ፡ ፩፤
በዮርዳኖስም ፡ ወንዝ ፡ ማዶና ፡ በባሕር ፡ዳርቻ ፡
የሚኖሩ ፡ የከራንና ፡ የገለዓድ ፡ የኢያቡሲዎንና ፡
የከናኔዎን ፡ የኤዶምና ፡ የጌርጌሴዎን ፡ የአማ
ሌቅ ፡ ሰዎች ፡ ናቸው ።
በየነገዳቸውና ፡ በየሀገራቸው ፡ በየአውራጃ ፪፤
ቸውና ፡ በየሥራቸውም ፡ በየሀገራቸውም ፡
ቋንቋ ፡ ጸንተው ፡ የሚኖሩ ፡ አሕዛብ ፡ ሁሉ ፡
እንዲህ ፡ ያደርጋሉ ፡ ሁሉም ፡ እግዚአብሔር ፡
እንደሠራቸው ፡ ጸንተው ፡ ይኖራሉ ።
ከነሳቸውም ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚያውቁት ፡ ፫፤
ሥራቸው ፡ ያማረ ፡ ሰዎች ፡ አሉ ።
ከነሳቸውም ፡ ሥራቸው ፡ ክፉ ፡ የሆነ ፡ የፈጠ ፬፤
ራቸው ፡ እግዚአብሔርንም ፡ የማያውቁት ፡
ሰዎች ፡ አሉ ፡ ኃጢአት ፡ እንደሠሩ ፡ በሰርያው ፡
ንጉሥ ፡ በስልምናሶርም ፡ እጅ ፡ ገዛቸው ።
የደማስቆን ፡ ገንዘብ ፡ ዘርፎ ፡ ይወስዳልና ፡ በግ ፭፤
ብፅ ፡ ንጉሥ ፡ ፊት ፡ ያለ ፡ የሠማርያንም ፡ ምርኮ ፡
ያከፍላልና ፡ በስልምናሶር ፡ እጅ ፡ ገዛቸው ።
የጌላቡሄ ፡ አውራጃና ፡ በገለዓድም ፡ አምባ ፡ ፮፤
የይሁዳ ፡ ምድር ፡ ክፍል ፡ በምትሆን ፡ ጳስጠ
ስም ፡ በምዕራብ ፡ ተራራ ፡ የሚኖሩ ፡ በፋርስና ፡
በሚዶን ፡ በቀጰዶቅያና ፡ በሲውሲግያ ፡ ሰዎች ።
በአውራጃቸውም ፡ የሚኖሩ ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ፡ ፯፤
እግዚአብሔርንም ፡ የማያውቁ ፡ ትእዛዙንም ፡
የማይጠብቁ ፡ ክፋደ ፡ ልቡናቸው ፡ የጸና ፡ ወገ
ኖች ፡ ናቸው ።
እሱም ፡ እንደ ፡ ሥራቸው ፡ ክፋት ፡ እንደ ፡ ፰፤
እጃቸውም ፡ ሥራ ፡ ፍዳቸውን ፡ ይ፤ ፍላቸዋል ።
የገለዓድ ፡ ወገኖችና ፡ የቂሣርያ ፡ አውራጃ ፡ አማ ፱፤
ሌቅም ፡ እውነት ፡ ነገርን ፡ የተመላች ፡ ከክበሩ ፡
የከበረ ፡ አሸናፊ ፡ የሚሆን ፡ በኪሩቤል ፡ ሠረገ
ላት ፡ የብዙ ፡ ብዙ ፡ የሚሆኑ ፡ መላእክት ፡ በፊቱ ፡
የሚቆሙ ፡ ፈርተው ፡ ተንቀጥቅጠው ፡ የሚያ
ገለግሉት ፡ የእስራኤል ፡ ፈጣሪ ፡ በውስጢ ፡ የሚ
መሰገንበት ፡ የእግዚአብሔርን ፡ አገር ፡ ያጠ
ፏት ፡ ዘንድ ፡ አንድ ፡ ሆነውበታልና ፡ እሱም ፡
እንደ ፡ ሥራቸው ፡ ክፋት ፡ እንደ ፡ እጃቸውም ፡
ሥራ ፡ ፍዳቸውን ፡ ይከፍላቸዋል ።

ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

የአማሌቅና ፡ የኢዶምያስን ፡ ሰዎች ፡ የምድ ፩፤
ርና ፡ የሰማይ ፡ አገዛዝ ፡ በሥልጣኑ ፡ የተያዘ ፡
እግዚአብሔርን ፡ አያመልኩትም ፡ እነሳቸው ፡
በውነት ፡ ሥራ ፡ ጸንተው ፡ የማይኖሩ ፡ ወንጀለ
ኞች ፡ ናቸውና ፡ ማደሪያው ፡ ቤተ ፡ መቅደስን ፡
ማፍረስ ፡ አይፈሩም ።

፪፤ ደም ፡ ከማፍሰስና ፡ ከገመ·ት ፡ የተመታውንና ፡
ለጣዖት ፡ የተሠዋውን ፡ ሙቶ ፡ ያደረውንም ፡
የሚመስለውን ፡ ሁሉ ፡ ከመብላት ፡ በቀር ፡ በፊ
ታቸውም ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ የለም ፡
እነዚህም ፡ የተናቁ ፡ ኃጢአተኞች ፡ ናቸው ።
፫፤ ምግባር ፡ ሃይማኖት ፡ የላቸውም ፡ በጎ ፡ ሥራን ፡
የጠሉ ፡ ናቸውና ፡ እግዚአብሔርንም ፡ አያው
ቁትምና ፡ የሰው ፡ ገንዘብ ፡ ከመቀማትና ፡ ከኃጢ
አት ፡ በቀር ፡ ሰውን ፡ ከማወክና ፡ ከሚጠላም ፡
ሥራ ፡ ሁሉ ፡ በቀር ፡ አባታቸው ፡ ዲያብሎስ ፡
እንዳስተማራቸው ፡ ከጨዋታና ፡ ከዘፈን ፡ በቀር ፡
የፍቅርንም ፡ ሥራ ፡ አያውቁምና ፡ ምግባር ፡
ሃይማኖት ፡ የላቸውም ።
፬፤ እሱ ፡ ከሠራዊቱ ፡ ከአጋንንት ፡ ጋራ ፡ ገዢቷቸ
ዋልና ፡ ለየራሱ ፡ የሆነ ፡ የክፉ ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡
የቅሚያና ፡ የኃጢአትን ፡ የስርቆትንና ፡ የሐ
ሰት ፡ ገንዘብ ፡ የመቀማትን ፡ አባላ ፡ የተመታው
ንና ፡ ሙቶ ፡ ያደረውን ፡ መብላትንም ፡ የዝሙ
ትንም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ያስተምራቸዋል ።
፭፤ ይኸንንም ፡ የሚመስለውን ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ጐል
ማሳ ፡ ሚስት ፡ መሔድንም ፡ ደም ፡ ማፍሰስንም ፡
ለጣዖት ፡ የተሠዋውን ፡ ሙቶ ፡ ያደረውን ፡ መብ
ላት ፡ የሰው ፡ ነፍስንም ፡ በግፍ ፡ መግደል ፡ ምቀኝ
ነትንና ፡ መጠቃቀስንም ፡ ስስትንም ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ የማይወደውን ፡ ክፉ ፡ ሥራንም ፡ ሁሉ ፡
ያስተምራቸዋል ፡ ዓለሙን ፡ ሁሉ ፡ ከሚገዛ ፡ ከእ
ግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ ያርቃቸው ፡ ዘንድ ፡ ጠላታ
ቸው ፡ የሆነ ፡ ዲያብሎስ ፡ ይኸንን ፡ ትምህርት ፡
ያስተምራቸዋል ።
፮፤ የእግዚአብሔር ፡ ሥራ ፡ ግን ፡ የዋህነትና ፡
ትሕትና ፡ ወንድምን ፡ አለማበሳጨትና ፡ በልንጀ
ራን ፡ መውደድ ፡ ከሰው ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ መስማ
ማትና ፡ መፋቀር ፡ ነው ።
፯፤ ለሰው ፡ ሬት ፡ ለማዳላት ፡ ግብዞችን ፡ አትሁን ፡
በደለኞችንም ፡ ፊጽማችሁም ፡ ቀማኞች ፡ ወደ ፡
ጐልማሳ ፡ ሚስት ፡ የሚሔዱ ፡ ሰዎችንም ፡ በባ
ልንጀራቸው ፡ ላይ ፡ በደልንና ፡ ክፉ ፡ ሥራን ፡
የሚሠሩ ፡ በግፍ ፡ በልንጀራቸውንም ፡ ይበድሉ ፡
ዘንድ ፡ የሚሸነግሉ ፡ ሰዎችንም ፡ አትሁኑ ።
፰፤ ይጠቃቀሳሉ ፡ ራሳቸውንም ፡ ይነቀንቃሉ ፡ ለክ
ፋትም ፡ ይተነኰሳሉ ፡ ሰዎችን ፡ ወደ ፡ ዘለዓለም ፡
ቍርጥ ፡ ፍርድ ፡ ያወርዷቸው ፡ ዘንድ ፡ ለማሳት ፡
ያሚርቃሉ ።

ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

፩፤ ሁሉ ፡ በእጁ ፡ ወዳለ ፡ በሞት ፡ ወደ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ እንድትሔድ ፡ አስብ ፡ በሠራኸውም ፡
ኃጢአት ፡ በፊቱ ፡ ይፈርድብህ ፡ ዘንድ ፡ አንተ ፡
በፊቱ ፡ ትቆማለህ ።
፪፤ ትዕቢተኞችና ፡ ክፉዎች ፡ የሚሆኑ ፡ ከነሳቸ
ውም ፡ የሚበልጥ ፡ የሚበረታ ፡ የሌለ ፡ የኃይለ
ኞች ፡ ልጆች ፡ ቀድሞ ፡ እንደዚሁ ፡ ነበርና ፡ ቁመ
ታቸውንና ፡ ኃይላቸውን ፡ ጽኑ ፡ ሥልጣናቸ
ውንም ፡ ስላዩ ፡ እግዚአብሔርን ፡ በፊታቸው ፡
አላደረጉትም ፡ እሱ ፡ ከለመኖር ፡ ወደ ፡ መኖር ፡
አምጥቶ ፡ የፈጠራቸው ፡ ፈጣሪያቸውም ፡ እንደ ፡
ሆነ ፡ አላወቁም ።
አባቶቻቸውም ፡ እንደ ፡ መላእክት ፡ ሁነው ፡ ፫፤
ከመላእክት ፡ ጋራ ፡ በደብር ፡ ቅዱስ ፡ ሲያመሰ
ግኑ ፡ ፈቃዳቸው ፡ ባስታቸው ፡ ጊዜ ፡ ለዘለዓ
ለሙ ፡ ቍርጥ ፡ ፍርድ ፡ ወደሚደረግበት ፡ ወደ
ዚህ ፡ ዓለም ፡ ወረዱ ።
ስለ ፡ ልቡናቸው ፡ ትዕቢት ፡ ያስታቸው ፡ ዘንድ ፡ ፬፤
ሕጉንና ፡ ትእዛዙንም ፡ ይጠብቁ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
ይፈትናቸው ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጥንቱን ፡
የሰው ፡ ሥጋ ፡ ፈጥሮላቸዋልና ፡ ከቃየል ፡ ልጆች ፡
ሚስት ፡ አገቡ ።
እነሳቸው ፡ ግን ፡ ሕጉን ፡ አልጠበቁም ፡ ከባታ ፭፤
ቸው ፡ ከዲያብሎስ ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡ እሳት ፡
አወረዳቸው ፤ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሰው ፡
የበደሉ ፡ ደቂቀ ፡ ሴትን ፡ ተቈጥቷቸዋልና ፡ ስለ
ነሳቸውም ፡ ኃጢአት ፡ የሰው ፡ ዘመኑ ፡ አነሰ ።
የአዳምንም ፡ ልጆች ፡ ከነሳቸው ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ ፮፤
ኃጢአት ፡ ወሰዷቸው ፡ እነሳቸው ፡ መቻያ ፡ ወደ
ሚቀበሉበት ፡ ወደ ፡ ሲኦል ፡ አወረዷቸው ።
የሴት ፡ ልጆች ፡ በቃየል ፡ ልጆች ፡ ስለ ፡ ሳቱ ፡ ፯፤
የሰው ፡ ዘመኑ ፡ ተከፍሏልና ፡ ጥንቱን ፡ የሰው ፡
ዘመኑ ፡ ዘጠኝ ፡ መቶ ፡ ሲሆን ፡ መቶ ፡ ሐያ ፡
ዘመን ፡ ወደ ፡ መኖር ፡ ተመለሰ ።
እነሳቸውም ፡ ሥጋውያን ፡ ደማውያን ፡ ናቸ ፰፤
ውና ፡ እግዚአብሔር ፡ መንፈሰ ፡ ረድኤቱ ፡ በነ
ሳቸው ፡ ጸንቶ ፡ አይኖርም ፡ አለ ።
ስለዚህም ፡ ነገር ፡ ዘመናችን ፡ ተከፈለ ፡ ስለ ፡ ፱፤
ኃጢአታችንና ፡ ስለ ፡ በደላችን ፡ ዘመናችን ፡
ከቀደሙ ፡ አባቶቻችን ፡ ተከፍሏልና ፡ ዳግመ
ኛም ፡ በሕፃንነት ፡ ሳሉ ፡ የሚሞቱ ፡ አሉ ።
ሕጉን ፡ ስለ ፡ ጠበቁ ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ስለ ፡ ፲፤
አላሳዘኑት ፡ የአባቶቻችን ፡ ዘመን ፡ ግን ፡ በዝቶ ፡
ነበር ።
ያስተምሯቸው ፡ ዘንድ ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻቸውን ፡ ፲፩፤
ስለ ፡ ተቈጡ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ እንዳያ
ፈርሱ ፡ ወንዶች ፡ ልጆቻቸውንም ፡ ስለ ፡ ተቈ
ጧቸው ፡ ያባቶቻችን ፡ ዘመን ፡ ግን ፡ በዝቶ ፡
ነበር ።
ከሴቶች ፡ ልጆቻቸውና ፡ ከወንዶች ፡ ልጆቻ ፲፪፤
ቸው ፡ ጋራ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ ስላላ
ፈረሱ ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ በውነት ፡ ዘመናቸው ፡
በዝቶ ፡ ነበር ።

ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

የቃየን ፡ ልጆች ፡ በበዙ ፡ ጊዜ ፡ ከበሮና ፡ በገ ፩፤
ናን ፡ ሳንቲንና ፡ መሰንቆን ፡ ሠሩ ፡ ዘፈንና ፡
ጨዋታውንም ፡ ሁሉ ፡ አደረጉ ።
እርሷ ፡ መልክ ፡ መልክም ፡ ነበረችና ፡ ስለእርሷ ፡ ፪፤
ከገደለው ፡ ከደግ ፡ ሰው ፡ ከአቤል ፡ ሚስት ፡
መልክ ፡ መልካሞች ፡ ደመ ፡ ግቡዎች ፡ የሚሆኑ ፡
ልጆች ፡ ዳግመኛ ፡ ለቃየን ፡ ተወለዱለት ፡ ወን
ድሙንም ፡ ከገደለው ፡ በኋላ ፡ የርሱ ፡ ገንዘብ ፡

የሆነች ፡ ያቺንና ፡ እቢን ፡ ወሰደ ።
፫፤ ከአባቱም ፡ ተለይቶ ፡ እነሳቸውን ፡ ይዞ ፡ በም
ዕራብ ፡ በኩል ፡ ወዳለ ፡ ወደ ፡ ቁፋዝ ፡ አው
ራጃ ፡ ሄደ ፡ የዚያች ፡ የመልክ ፡ መልክም ፡ ልጆ
ችም ፡ እንደ ፡ እናታቸው ፡ መልከ ፡ መልከ
ሞች ፡ ሆኑ ።
፬፤ ስለዚህም ፡ ነገር ፡ የሴት ፡ ልጆች ፡ ወደ ፡ ቃየን ፡
ልጆች ፡ ወረዱ ፡ ከይዋቸውም ፡ በኋላ ፡ አንዲት ፡
ሰዓት ፡ አልቈዩም ፡ የመረጧቸውንም ፡ ሴቶች ፡
ለራሳቸው ፡ ሚስት ፡ አደረጉ ።
፭፤ ስለ ፡ ስሕተታቸው ፡ ከነሳቸው ፡ ጋራ ፡ አንድ
ነት ፡ ወደ ፡ ስሕተት ፡ ወስደውናልና ፡ ስለዚህ ፡
ነገር ፡ እግዚአብሔር ፡ እኛን ፡ ተቈጣን ፡ እነሳ
ቸውንም ፡ ተቈጣቸው ።
፮፤ ዲያብሎስም ፡ እንደ ፡ ፈጣሪያችሁ ፡ እንደ ፡
እግዚአብሔር ፡ ፈጣሪዎችን ፡ ትሆናላችሁ ፡
ብሎ ፡ ሸንግሎ ፡ እናታችን ፡ ሔዋንን ፡ አባታ
ችን ፡ አዳምን ፡ ወደርሱ ፡ ስሕተት ፡ ወሰዳቸው ።
፯፤ እነርሳቸው ፡ ግን ፡ በድንቍርናቸው ፡ እውነት ፡
መስሏቸው ፡ ይሰግዱ ፡ ዘንድ ፡ የከበረ ፡ ስሙ
ንም ፡ ያመሰግኑ ፡ ዘንድ ፡ ከለመኖር ፡ ወደ ፡
መኖር ፡ አምጥቶ ፡ የፈጠራቸውን ፡ የእግዚአ
ብሔርን ፡ ሕግ ፡ አፈረሱ ።
፰፤ አምላክነትን ፡ ለራሳቸው ፡ ያደረጉ ፡ እነዚያን ፡
ሔዋንና ፡ አዳምን ፡ ግን ፡ እሱ ፡ ፈጣሪያቸው ፡
አዋረዳቸው ፡ ትዕቢተኛ ፡ የሚሆን ፡ እሱንም ፡
አዋረደው ።
፱፤ ዳዊት ፡ በኃጢአተኛ ፡ ዲያብሎስ ፡ ትዕቢት ፡
አዳም ፡ ይጠፋል ፡ ብሎ ፡ እንደተናገረ ፡ አባታ
ችን ፡ አዳም ፡ በዲያብሎስ ፡ ትዕቢት ፡ ከእግዚ
አብሔር ፡ በታዘዘ ፡ በውነተኛ ፡ ፍርዱ ፡ ተፈር
ዶበታልና ፡ አገለሰቈላቸው ።
፲፤ በቃየል ፡ ልጆች ፡ የሳቱ ፡ የሴት ፡ ልጆችም ፡
እንዲሁ ፡ ወደ ፡ ኃጢአታቸው ፡ ወሰዱን ፡ ስለ
ዚህ ፡ ነገር ፡ እግዚአብሔር ፡ የሰጠን ፡ ዘመና
ችን ፡ ከአባቶቻችን ፡ ዘመን ፡ አነሰ ።
፲፩፤ እነሳቸው ፡ ግን ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ ሠርተው ፡ ነበር ፡
ልቡናቸውን ፡ በእግዚአብሔር ፡ አጽንተው ፡
ነበርና ፡ ከስተማሯቸው ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡
እንዳይወጡ ፡ ሴቶች ፡ ልጆቻቸውንና ፡ ወን
ዶች ፡ ልጆቻቸውንም ፡ አስተምረው ፡ ነበርና ፡
የሚቀርባቸው ፡ ክፉ ፡ ጠላትም ፡ አልነበረ ።
፲፪፤ እነሳቸው ፡ ግን ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ ቢሠሩ ፡ ለልጆቻ
ቸው ፡ ክልነገሩ ፡ ከላስተማሯቸው ፡ የሚጠቅማ
ቸው ፡ የለም ።
፲፫፤ ዳዊት ፡ ከልጆቻቸው ፡ ለሌላ ፡ ልጅ ፡ አልሠወ
ሩም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ምስጋና ፡ ያደረገውን ፡
ድንቅ ፡ ታምራትና ፡ ኃይሉንም ፡ አስተማሩ ፡
ብሎ ፡ እንዳ ፡ ተናገረ ፡ እነሳቸው ፡ እንዳወቁ ፡
ልብ ፡ ሊያደርጉ ፡ ለልጆቻቸው ፡ ያስተምሩ ፡
ዘንድ ፡ አወ/ቀውም ፡ ፈቃዱን ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡
የእግዚአብሔር ፡ ሕጉንም ፡ አደራ ፡ ይሏቸው ፡
ዘንድ ፡ በማረ ፡ ሥራቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡
ደስ ፡ እንዳሰኙት ፡ እንደ ፡ አባቶቻቸውም ፡
ሕጉን ፡ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ፡ ለልጆቻቸው ፡ ከላስ
ተማሩ ፡ የሚጠቅማቸው ፡ የለም ።
ከባቶቻቸው ፡ በሕፃንነታቸው ፡ አደራ ፡ ያልዋ ፲፬፤
ቸው ፡ ትእዛዙንም ፡ አላፈረሱም ፡ አባቶቻቸው ፡
ከባቶቻቸው ፡ የእግዚአብሔርን ፡ አምልኮት ፡
ዘጠኙንም ፡ ሕግጋት ፡ እንደ ፡ ተማሩ ።
በጎ ፡ ሥራ ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ለፈጣሪያቸውም ፡ ፲፭፤
ምስጋናን ፡ ያቀርቡ ፡ ዘንድ ፡ ልጆቻቸው ፡ ከበ
ቶቻቸው ፡ ተማሩ ፡ ሕጉን ፡ ጠብቀዋልና ፡ እሱ
ንም ፡ ወደውታልና ።
እሱም ፡ ጸሎታቸውን ፡ ይሰማቸዋል ፡ ልመናቸ ፲፮፤
ውንም ፡ ቸል ፡ አይልም ፡ እሱ ፡ ግን ፡ ይቅር ፡
ባይ ፡ ነው ።
መዓቱን ፡ አብዝቶ ፡ ይመልስላቸዋል ፡ በመቅ ፲፯፤
ሠፍቱም ፡ ሁሉ ፡ አያጠፋም ፡ ነበር ።

ምዕራፍ ፡ ፳ ።

ወንድሞቻችን ፡ አስቡ ፡ እግዚአብሔር ፡ በጎ ፡ ፩፤
ሥራ ፡ የሚሠሩ ፡ ሰዎችን ፡ እውነተኛ ፡ ሥራቸ
ውን ፡ እንዲጠብቅ ፡ ቀድሞ ፡ የነገሩዋችሁን ፡
አትርሱ ።
ልጆቻቸውንም ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ያበዛል ፡ ስም ፡ ፪፤
አጠራራቸውም ፡ ለበጎ ፡ ነገር ፡ እስከ ፡ ዘለዓ
ለሙ ፡ ድረስ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፡ ልጃቸውም ፡
በዚህ ፡ ዓለም ፡ እህልን ፡ አይቸገርም ።
ስለነሳቸው ፡ ይከራከርላቸዋልና ፡ በጠላታቸ ፫፤
ውም ፡ እጅ ፡ አይጥላቸውምና ፡ ከሚጠሏቸው ፡
ከጠላቶቻቸው ፡ እጅ ፡ ያድናቸዋል ።
ስሙን ፡ ለሚወዱ ፡ ሰዎችም ፡ በመከራቸው ፡ ፬፤
ጊዜ ፡ ረዳት ፡ ይሆናቸዋል ፡ ይጠብቃቸዋል ፡
ኃጢአታቸውንም ፡ ሁሉ ፡ ይቅር ፡ ይላቸዋል ።

ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

ዳዊት ፡ በእግዚአብሔር ፡ አመነ ፡ በሱ ፡ አም ፩፤
ኗልና ፡ መጠጊያ ፡ ሆነው ፡ ከንጉሡ ፡ ከሳኦልም ፡
እጅ ፡ አዳነው ።
ልጁ ፡ አቤሴሎም ፡ በተነሣበት ፡ ጊዜ ፡ ኢሎፍ ፪፤
ላውያንም ፡ በተነሡበት ፡ ጊዜ ፡ ኤዶማውያ
ንና ፡ አማሌቃውያንም ፡ በተነሡበት ፡ ጊዜ ፡
ከራቱ ፡ ራፋይን ፡ አንዱ ፡ በተነሣበት ፡ ጊዜ ፡ በሱ ፡
አምኗልና ፡ ሕጉንም ፡ ጠብቋልና ፡ የተከራከሩት ፡
ጠላቶች ፡ ከመጡበት ፡ ከዚህ ፡ ሁሉ ፡ መከራ ፡
እግዚአብሔር ፡ ዳዊትን ፡ አዳነው ።
ድል ፡ መንሣት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ ፫፤
ነውና ፡ በጠላቶቻቸው ፡ እጅ ፡ ድል ፡ ተነሡ ፡
እንጂ ፡ ያላመኑበት ፡ ክፉ ፡ የሆኑ ፡ ነገሥታቱን ፡
ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ አላዳናቸውም ።
ሕዝቅያስም ፡ በእግዚአብሔር ፡ አመነ ፡ ትዕቢ ፬፤
ተኛ ፡ ከሆነ ፡ ከሰናክሬም ፡ እጅ ፡ አዳነው ።
መታመኑን ፡ በእግዚአብሔር ፡ አላደረገምና ፡ ፭፤
ልጁ ፡ ምናሴ ፡ ግን ፡ በጠላቱ ፡ እጅ ፡ ድል ፡ ተነሣ ፡
መታመኑን ፡ በእግዚአብሔር ፡ አላደረገምና ፡
ፈጽሞ ፡ ያከበረው ፡ ያገነነው ፡ እግዚአብሔር
ንም ፡ አልፈራውምና ፡ አሥረው ፡ ወደ ፡ አገሩ

ቸው ፡ ወሰዱት ፡ እንጂ ፡ ምናሴን ፡ ድል ፡ የነ
ሡት ፡ እነዚያ ፡ ጠላቶቹ ፡ ግን ፡ እንደሱ ፡ አል
ሆኑም ።
፮፤ ዘመኑ ፡ ይበዛ ፡ ዘንድ ፡ ጠላቱንም ፡ ይከራከር
ለት ፡ ዘንድ ፡ በኋላና ፡ በፊትም ፡ ኃይልን ፡ ጽን
ዕን ፡ ይሆነው ፡ ዘንድ ፡ በፈጣሪው ፡ በእግዚአ
ብሔር ፡ ፊት ፡ በጎ ፡ ሥራን ፡ አልሠራምና ፡ የሰ
ጠውን ፡ መንግሥት ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ነሣው ።
፯፤ ከብዙ ፡ ሠራዊት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ማመን ፡
ይሻላልና ፡ በፈረሶች ፡ በቀስትና ፡ በጋሻ ፡ ከማ
መን ።
፰፤ በእግዚአብሔር ፡ ማመን ፡ ይበልጣል ፡ በሱ ፡
ያመነ ፡ ሰው ፡ ይጸናል ፡ ይከብራል ፡ ፈጽሞም ፡
ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ።
፱፤ እግዚአብሔር ፡ ለፊት ፡ አያደላምና ፡ በእግዚአ
ብሔር ፡ ያላመኑ ፡ በገንዘባቸው ፡ ብዛት ፡ ያመኑ ፡
ሰዎች ፡ ግን ፡ ከሰጣቸው ፡ ጸጋና ፡ ክብር ፡ የወጡ ፡
ሆኑ ።
፲፤ ያመኑበትን ፡ ሰዎች ፡ ይጠብቃቸዋል ፡ ያላዋቂ ፡
የሚሉትን ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ያላዋቂ ፡ ያደርጋቸ
ዋል ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለመከተል ፡ ሕጉንም ፡
ለመጠበቅ ፡ ልቡናቸውንም ፡ አላስጨከኑምና ፡
በመከራቸው ፡ ጊዜ ፡ ጠላቶቻቸውም ፡ በተከራ
ከሩዋቸው ፡ ጊዜ ፡ ፈጥኖ ፡ አይረዳቸውም ።
፲፩፤ እግዚአብሔርን ፡ በማምለክ ፡ ሕጉንም ፡ ለመጠ
በቅ ፡ ለጨከነ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ በመከራው ፡ ጊዜ ፡
መጠጊያን ፡ ይሆነዋል ።
፲፪፤ ጠላቱን ፡ በማጥፋት ፡ የጠላቱንም ፡ ከብት ፡ በመ
ዝረፍ ፡ የጠላቱን ፡ አገር ፡ ሰውም ፡ በመማረክ ፡
የዘመኖች ፡ ዝናምንም ፡ በማዝነም ፡ ቡቃያንም ፡
በማብቀል ፡ የእህሉንም ፡ ክምር ፡ በማግበት ፡
በተክሉ ፡ ፍሬ ።
፲፫፤ የሳተኑንና ፡ የበልጉንም ፡ ዝናም ፡ በማዝነም ፡
ማሩንም ፡ በማለምለም ፡ ከሥልጣንህ ፡ በታች ፡
ያሉ ፡ ወገኖችህ ፡ ደስ ፡ ይላቸው ፡ ዘንድ ፡ በየ
ጊዜውም ፡ የሚዘንመውን ፡ ዝናም ፡ በመስጠት ፡
ደስ ፡ ያሰኘዋል ።
፲፬፤ የሌላውን ፡ ገንዘብ ፡ ይበሉ ፡ ዘንድ ፡ ከጠላታ
ቸው ፡ የዘረፉትን ፡ ገንዘብ ፡ በልተው ፡ ይጠ
ግቡ ፡ ዘንድ ፡ እንስሳትን ፡ በጎችንና ፡ ላሞች
ንም ፡ ይዘርፉ ፡ ዘንድ ፡ የሌላውንም ፡ ማዕድ ፡
ይበሉ ፡ ዘንድ ፡ የጠላቶቻቸውንም ፡ ልጆች ፡
ምርኮ ፡ ይወስዱ ፡ ዘንድ ፡ ደስ ፡ ያሰኘዋል ።
፲፭፤ እግዚአብሔር ፡ ይኸን ፡ ሁሉ ፡ ለሚወደው ፡ ሰው ፡
ያደርግለታል ፡ የሚጠላውን ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ለጠ
ላቱ ፡ ብዝበዛ ፡ ያደርገዋል ።
፲፮፤ እግሩንና ፡ እጁንም ፡ ያሥረዋል ፡ በጠላቱም ፡
እጅ ፡ ይጥለዋል ፡ ለጠላቶቹም ፡ መዘበበቻ ፡
ያደርገዋል ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ ያፈረሰ ፡
ደም ፡ አፍሳሽም ፡ ሆኗልና ፡ በቤቱ ፡ ዘር ፡ ደስ ፡
አያሰኘውም ።
፲፯፤ በፍርድም ፡ ጊዜ ፡ አይጸናም ፡ ኃጢአትንም ፡
ለሚሠሩ ፡ ሰዎች ፡ ፍዳውን ፡ ያመጣባቸው ፡
ዘንድ ፡ ክፉ ፡ ሥራን ፡ ለሚሠሩ ፡ ሰዎችም ፡
የኃጢአታቸውን ፡ ፍዳ ፡ ይሰጣቸዋል ።
በሥልጣኑ ፡ ይጠብቃቸው ፡ ዘንድ ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ ፲፰፤
ለሚሠሩ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ዋጋቸውን ፡ ሊሰጣ
ቸው ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ታዝዞ ።
በጎ ፡ ሥራን ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ የዘለዓለም ፡ ድኅ ፲፱፤
ነትንም ፡ ይሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ እነሳቸውም ፡ የፈ
ጠራቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመሰግኑት ፡
ዘንድ ፡ እሱ ፡ በፈጠረው ፡ ፍጥረት ፡ ሁሉ ፡
ላይ ፡ ከሀሊ ፡ ነውና ፡ እሱም ፡ ሕጉን ፡ ይጠ
ብቅ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፡ ከሰው ፡ ብቻ ፡ በቀር ፡ ከፈ
ጠረው ፡ ፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ ከትእዛዙ ፡ የወጣ ፡
የለም ።
እግዚአብሔር ፡ በየሥራቸው ፡ ጸንተው ፡ የሚ ፳፤
ኖሩትን ፡ ሁሉ ፡ እንዳዘዛቸው ፡ ሁሉም ፡ አው
ቀው ፡ በሕጉ ፡ ይጠበቃሉ ።
ሰው ፡ ግን ፡ በየፈጠራቸው ፡ በእንስሳና ፡ በአራ ፳፩፤
ዊት ፡ ላይ ፡ በሰማይም ፡ ወፎች ፡ ላይ ፡ ሁሉ ፡
በነገሠው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ ይደፋፈራል ።
በባሕር ፡ ያለውን ፡ በየብስ ፡ ያለውንም ፡ ሁሉ ፡ ፳፪፤
ቢሆን ፡ የፈጠረውን ፡ ፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ላበታቸው ፡ ለአዳም ፡ ሰጠው ፡ የወ
ደደውን ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ በምድርም ፡ እንደ
በቀለ ፡ እህል ፡ ይበሏቸው ፡ ዘንድ ፡ ገዝተውም ፡
ያስገብሯቸው ፡ ዘንድ ፡ አራዊትም ፡ ቢሆኑ ፡
እንስሳትም ፡ ቢሆኑ ፡ ለሰው ፡ ይታዘዙ ፡ ዘንድ ፡
እግዚአብሔር ፡ ሰጣቸው ፡ የነገሡ ፡ ሰዎችም ፡
ክብርን ፡ ለሰጣቸው ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ይታዘዙ ፡
ዘንድ ፡ ያደሉለትም ፡ ዘንድ ፡ በፈጠረው ፡ ሁሉ ፡
ላይ ፡ ሾማቸው ።
ከሕጉ ፡ ቢወጡ ፡ ግን ፡ እሱ ፡ ከሰጣቸው ፡ ጌት ፳፫፤
ነት ፡ ይለያቸዋል ፡ ምድርንና ፡ ሰማይን ፡ የሚ
ገዛ ፡ ነውና ፡ ፈቃዱን ፡ ለሚያደርግ ፡ ይሰጠዋል ።
ሊሾመው ፡ የወደደውን ፡ ይሾመዋል ፡ ሊሽ ፳፬፤
ረው ፡ የወደደውን ፡ ግን ፡ ይሽረዋል ፡ ይገድ
ላል ፡ ያድናል ፡ በመከራ ፡ ይገርፋል ፡ ይቅር ፡
ይላል ።
እንደሱ ፡ ያለ ፡ ፈጣሪ ፡ ሌላ ፡ የለም ፡ ለፈጠ ፳፭፤
ረው ፡ ፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ እሱ ፡ ገዥ ፡ ነውና ፡
ከምድር ፡ በላይ ፡ ባለ ፡ በሰማይ ፡ ከሰማይ ፡
በታች ፡ ባለ ፡ በምድር ፡ ያለሱ ፡ ፈጣሪ ፡ ሌላ ፡
የለምና ፡ የሚነቅፈው ፡ የለም ።
ይሾማል ፡ ይሽራል ፡ ይገድላል ፡ ያድናል ፡ በመ ፳፮፤
ከራ ፡ ይገርፋል ፡ ይቅር ፡ ይላል ፡ ያደኸያል ፡
ያከብራል ።
የሚለምኑትን ፡ ሰዎች ፡ ልመናቸውን ፡ ይሰማ ፳፯፤
ቸዋል ፡ በንጽሕ ፡ ልቡና ፡ ፈቃዱን ፡ የሚያደር
ግን ፡ ሰው ፡ ልመናውን ፡ ይቀበለዋል ፤ እሱም ፡
ጸሎታቸውን ፡ ይሰማቸዋል ፡ በለመኑትም ፡
ሁሉ ፡ ፈቃዳቸውን ፡ ያደርግላቸዋል ።
ታላቁንና ፡ ታናሹንም ፡ እንዲታዘዙላቸው ፡ ያደ ፳፰፤
ርጋል ፡ በከረብታና ፡ በተራራ ፡ ላይ ፡ በዛፎች ፡
ሥርና ፡ በዋሻም ፡ በምድር ፡ ጕድጓድም ፡ በደረ
ቅና ፡ በባሕርም ፡ ያሉ ፡ ወገኖቻቸውንም ፡ ሁሉ ፡
ይህ ፡ ሁሉ ፡ የነሳቸው ፡ ገንዘብ ፡ ነው ።

፲፱፤ የፈጣሪያቸውንም ፡ ፈቃድ ፡ ለሚያደርጉ ፡
ሰዎች ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ ገንዘባቸው ፡ ነው ፡ ከበረከ
ቱም ፡ አያስቸግራቸውም ፡ የምስጋናቸውንም ፡
ዋጋ ፡ ይሰጣቸዋል ።
፳፤ በሰማይም ፡ ላባቶቻቸው ፡ ለይስሐቅና ፡ ለአብ
ርሃም ፡ ለያዕቆብም ፡ ያዘጋጀውን ፡ ክብር ፡ ይሰ
ጣቸዋል ፡ ከሕጉና ፡ ከትእዛዙ ፡ ላልወጡ ፡ ለሕ
ዝቅያስና ፡ ለዳዊት ፡ ለሳሙኤልም ፡ ያዘጋጀ
ውን ፡ ይሰጣቸዋል ።
፳፩፤ በጌትነቱ ፡ ደስ ፡ ይላቸው ፡ ዘንድ ፡ ከጥንት ፡
ጀምሮ ፡ ላገለገሉት ፡ ርስትን ፡ ሊሰጣቸው ፡ ለማ
ለላቸው ፡ ለአባቶቻቸው ፡ ለይስሐቅና ፡ ለአብር
ሃም ፡ ለያዕቆብም ፡ ያዘጋጀውን ፡ ክብር ፡ ይሰ
ጣቸዋል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩፤ በጎ ፡ ሥራን ፡ የሚሠሩትን ፡ ሰዎች ፡ ስም ፡
እስኪ ፡ እስብ ፡ ሥራቸውንም ፡ አትዘንጋ ።
፪፤ የእግዚአብሔርን ፡ ፈቃድ ፡ ላደረጉ ፡ ደጋጎች ፡
ሰዎች ፡ ለሆኑ ፡ ለመኳንንትና ፡ ለነገሥታት ፡
በዘጋጃት ፡ የብርሃን ፡ ማደሪያ ፡ በሆነች ፡ በመን
ግሥት ፡ ሰማይ ፡ ከነሳቸው ፡ ጋራ ፡ ደስ ፡ ይልህ ፡
ዘንድ ፡ ስምህ ፡ እንደ ፡ ስማቸው ፡ እንዲጠራ ፡
ቅና ።
፫፤ ዳግመኛም ፡ እንዲፈረድባቸው ፡ ከሞቱም ፡
በኋላ ፡ በሰው ፡ ዘንድ ፡ እንዲያሟቸው ፡ ክፉ
ዎች ፡ የመኳንንትና ፡ የነገሥታትን ፡ ስማቸውን ፡
ዕወቅ ፡ ተረዳ ።
፬፤ እያዩ ፡ እየሰሙ ፡ ሥራቸውን ፡ አላሠመሩምና ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ፈቃድ ፡ ካላደረጉ ፡ ከወንጀ
ለኞችና ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ ከዘነጉ ፡
ሰዎች ፡ በመንግሥት ፡ ሰማይም ፡ እንዲፈረድ
ባቸው ፡ ዕወቅ ፡ ተረዳ ።
፭፤ ቸር ፡ የዋህ ፡ ቅን ፡ ሁን ፡ እንኚ ፡ አንተም ፡ ስለ ፡
ክፉ ፡ ሥራቸው ፡ እግዚአብሔር ፡ በተቈጣቸው ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ በዘነጉ ፡ ሰዎች ፡ ጐዳና ፡
አትሒድ ።
፮፤ እውነትን ፡ ፈርደህ ፡ እናት ፡ አባቱ ፡ የሞቱበት ፡
ልጅንና ፡ ባልቴቷቱን ፡ ከሚቀሟቸው ፡ ከኃጢ
አተኞች ፡ ሰዎች ፡ እጅ ፡ አድን ።
፯፤ ከሚቀማው ፡ ከባለጠጋው ፡ እጅ ፡ ታድነው ፡
ዘንድ ፡ እናት ፡ አባቱም ፡ ለሞቱበት ፡ ልጅ ፡
እንደ ፡ አባቱ ፡ ጠበቃ ፡ ሁነው ፡ ቁምለትም ፡
ንስሐ ፡ ያልገቡ ፡ ኃጢአተኞችን ፡ ሰዎች ፡ በሚ
ቀጡበት ፡ በእሳት ፡ ባሕር ፡ እንዳትደነግጥ ፡
እናት ፡ አባቱ ፡ የሞቱበት ፡ ልጅ ፡ እንባም ፡ በፊ
ትህ ፡ በፈሰሰ ፡ ጊዜ ፡ ደንግጥ ።
፰፤ እግርህንም ፡ ወደ ፡ ፍቅር ፡ አንድነት ፡ ጐዳና ፡
አቅና ፡ የእግዚአብሔር ፡ ዓይኖች ፡ ወዳጆቹን ፡
ይመለከቷቸሉና ፡ ጆሮውም ፡ ልመናቸውን ፡ ይሰ
ማልና ፡ ፍቅርን ፡ ፈልጋት ፡ ተከተላት ።
፱፤ የእግዚአብሔር ፡ ገጹ ፡ መዓቱ ፡ ግን ፡ ስም ፡ አጠ
ራራቸውን ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ያጠፉ ፡ ዘንድ ፡
ክፉ ፡ ሥራን ፡ ወደሚሠሩ ፡ ሰዎች ፡ ነው ፡ በቅ
ጥርና ፡ በተራራ ፡ ላይ ፡ ያለ ፡ የሚጠጋ ፡ ሰው
ንም ፡ አያስቀርም ።
በአምላክነቱ ፡ የምቀና ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝና ፡ ፲፤
የሚጠሉኝ ፡ ቃሌንም ፡ የማይጠብቁ ፡ ሰዎችን ፡
ተበቅዬ ፡ የማጠፋ ፡ ፈጣሪ ፡ ነኝና ፡ ቃሌን ፡ የማ
ይጠብቅ ፡ ሰውን ፡ እስክጠፉው ፡ ድረስ ፡ ደርሴ ፡
ገጼ ፡ ረድኤቴን ፡ አልመልስም ።
የሚያከብሩኝንም ፡ ቃሌንም ፡ የሚጠብቁ ፡ ሰዎ ፲፩፤
ችን ፡ አከብራቸዋለሁ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

ወንድሙ ፡ የሚወደው ፡ መስሎት ፡ በየዋህ ፩፤
ነት ፡ የተከተለው ፡ ወንድሙን ፡ በገደለው ፡ በቃ
የል ፡ ሥርዓት ፡ ጸንተህ ፡ አትኑር ።
እርሱም ፡ በሴት ፡ ቀንቶ ፡ ወንድሙን ፡ ገደለው ፡ ፪፤
ቅናትና ፡ በደልን ፡ በባልንጀራቸውም ፡ ክዳ
ትን ፡ የሚያደርጉ ፡ ሰዎች ፡ እንደሱ ፡ ናቸው ።
አቤል ፡ ግን ፡ እንደ ፡ በግ ፡ የዋህ ፡ ነውና ፡ ፫፤
ደሙም ፡ በንጹሕ ፡ ልቡና ፡ ለእግዚአብሔር ፡
እንደሠጠት ፡ እንደ ፡ ንጹሕ ፡ በግ ፡ ደም ፡
ነውና ፡ በአቤል ፡ ጎዳና ፡ ያይደለ ፡ በቃየል ፡
ጐዳና ፡ ሄዱ ።
በየዋህነት ፡ የሚኖረውን ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ እግዚ ፬፤
አብሔር ፡ እንደ ፡ ደግ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ አቤል ፡
የሚወደው ፡ ሰው ፡ ስለሆነ ፡ እንደ ፡ አቤል ፡ የዋ
ሆችን ፡ ሆነዋልና ፡ የዋህ ፡ በሆነ ፡ በአቤል ፡
ሥራ ፡ ጸንተው ፡ የሚኖሩ ፡ እሊያ ፡ ሰዎች ፡
ግን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ይወዱታል ።
ክፉዎችን ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ቸል ፡ ይላቸ ፭፤
ዋል ፡ ቍርጥ ፡ ፍርዳቸውም ፡ በሰውነታቸው ፡
ደጅ ፡ ይጠናቸዋል ፡ በመትከፈ ፡ ልቡናቸውም ፡
የተጻፈ ፡ ነው ፡ ፍርድም ፡ በሚፈረድበት ፡ ጊዜ ፡
በሰውና ፡ በመላእክት ፡ ፊት ፡ በፍጥረቱም ፡
ሁሉ ፡ ፊት ፡ ያነቢታል ።
የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ያፍራሉ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ፮፤
ፈቃድ ፡ ያላደረጉ ፡ በደለኞችና ፡ እምቢተኞች ፡
ያፍራሉ ።
እስከ ፡ ዘለዓለሙ ፡ ድረስ ፡ መውጫ ፡ በሌለበት ፡ ፯፤
በገሃነም ፡ አኑሯቸው ፡ የሚል ፡ የሚያስደነግጥ ፡
ቃልም ፡ ይሰጣቸዋል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

ጌዴዎን ፡ ግን ፡ እግዚአብሔርን ፡ በታመነው ፡ ፩፤
ጊዜ ፡ በጥቂት ፡ ሠራዊት ፡ እልፍ ፡ የብዙ ፡ ብዙ ፡
የሆኑ ፡ እንዳንበጣም ፡ ቍጥር ፡ የሌላቸው ፡
ያልተገረዙ ፡ የአሕዛብን ፡ ሠራዊት ፡ ድል ፡ ነሣ ።
ያለኔ ፡ ፈጣሪ ፡ የለምና ፡ መኳንንትና ፡ ነገሥ ፪፤
ታት ፡ ሆይ ፡ ልዩ ፡ የሆኑ ፡ ጣዖታትን ፡ አትመኑ ።
ከናታችሁ ፡ ማኅፀን ፡ ያወጣኋችሁ ፡ ያሳደግኋ ፫፤
ችሁ ፡ የመገብኋችሁ ፡ ያለበስኋችሁ ፡ እኔ ፡ ፈጣ
ሪያችሁ ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝና ፡ ለምን ፡
ታመክኛላችሁ ፡ ያለኔስ ፡ ሌላ ፡ ጣዖትን ፡ ለምን ፡
ታመልክላችሁ ።
ይኽን ፡ ሁሉ ፡ አደረግሁላችሁ ፡ ምን ፡ ሰጣች ፬፤

ሁኝ ፡ በሕጌ ፡ በሥርዓቴ ፡ በትእዛዜ ፡ ጸንታችሁ ፡
ትኖሩ ፡ ዘንድ ፡ አኔም ፡ የሰውነታችሁን ፡ ድኅ
ነት ፡ እሰጣችሁ ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ከናንተ ፡
ምን ፡ እሻለሁ ።
፭፤ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡
ጣዖት ፡ ከማምለክ ፡ ጥንቈላም ፡ ከማስጠንቈል ፡
ሟርትም ፡ ከማሟረት ፡ ራሳችሁን ፡ አድኑ ፡
አለ ።
፮፤ በነዚህ ፡ ይህን ፡ በሚያደርጉ ፡ በሚሰሟቸውም ፡
ፈቃዳቸውን ፡ በሚያደርጉ ፡ ወዳጅም ፡ በሚሆ
ኗቸው ፡ በትእዛዛቸውም ፡ ጸንተው ፡ በሚኖሩ ፡
የእግዚአብሔር ፡ መቅሠፍት ፡ ይመጣልና ፡ ራሳ
ችሁን ፡ ጣዖት ፡ ከማምለክ ፡ አድኑ ።
፯፤ የማያውቋችሁ ፡ የማይራሩላችሁ ፡ አሕዛብ ፡
ይነሡባችኋልና ፡ የፈራችሁ ፡ የእግዚአብሔ
ርን ፡ ፈቃድ ፡ ካላደረጋችሁ ፡ የደከማችሁበትን ፡
ገንዘብ ፡ ይበላሉ ፡ ከነቢዩ ፡ ከሳሙኤል ፡ ጀምሮ ፡
አገልጋዮቹ ፡ ነቢያት ፡ እንደ ፡ ተናገሩ ፡ ዳግመ
ኛም ፡ ሕዝቅኤል ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ ሄኖክም ፡
እንደ ፡ ተናገረ ፡ አሳፍም ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ የእ
ግዚአብሔርን ፡ ፈቃድ ፡ ካላደረጋችሁ ፡ የደከ
ማችሁበትን ፡ ገንዘብ ፡ ይበላሉ ።
፰፤ ክፉ ፡ ሰዎች ፡ ልብሳቸውን ፡ ለውጠው ፡ ይመ
ጣሉ ፡ አለ ፡ ከመብላት ፡ ከመጠጣት ፡ በብርና ፡
በወርቅም ፡ ከማጌጥ ፡ እግዚአብሔርም ፡ የማይ
ወደውን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ በኃጢአት ፡ ጸንቶ ፡
ከመኖር ፡ በቀር ፡ በነሳቸው ፡ ዘንድ ፡ ሌላ ፡ ሕግ ፡
የለም ።
፱፤ እነሳቸው ፡ ግን ፡ ወደ ፡ መጠጥና ፡ ወደ ፡ መብል ፡
ለመሄድ ፡ የተዘጋጁ ፡ ናቸው ፡ ከንቅልፋቸው ፡
ከተቀሰቀሱ ፡ በኋላ ፡ ከጧት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡
ማታ ፡ ወደ ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ ይሄዳሉ ፤ በጐዳና
ቸው ፡ ጕስቍልና ፡ መከራ ፡ አለ ፡ እንጂ ፡ ለእግ
ራቸው ፡ የፍቅር ፡ ጐዳና ፡ የለውም ።
፲፤ የፍቅር ፡ አንድነት ፡ ሥራንም ፡ አያውቁትም ፡
በፊታቸውም ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡
የለም ፡ ሃይማኖትና ፡ ምግባር ፡ የሌላቸው ፡ ጠማ
ሞች ፡ ክፉዎች ፡ ናቸው ፡ ብቻቸውን ፡ የሚ
በሉ ፡ የሚጠጡ ፡ ስስታሞች ፡ ናቸው ፡ የሚሰ
ክሩ ፡ ናቸው ፡ ኃጢአታቸውም ፡ ያለ ፡ ሕግ ፡
ያለ ፡ መጠን ፡ ነው ፡ ወደ ፡ መዳራት ፡ ደም ፡ ወደ ፡
ማፍሰስ ፡ ወደ ፡ ስርቆሽ ፡ ወደ ፡ መክዳትም ፡
በግፍ ፡ የሌላውንም ፡ ገንዘብ ፡ ወደ ፡ መቀማት ፡
የሚሄዱ ፡ ናቸው ።
፲፩፤ ያለ ፡ ፍርድና ፡ ያለ ፡ ሕግም ፡ የሚወቅሱ ፡ ናቸው ፡
የፈጠራቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ አይፈሩትምና ፡
በፊታቸውም ፡ ፍራት ፡ የለም ።
፲፪፤ በሚያዩት ፡ የሰውን ፡ ፊት ፡ አያፍሩም ፡ የሽበ
ታም ፡ የሽማግሌ ፡ ፊትንም ፡ አያፍሩም ፡ በዚህ ፡
ዓለምም ፡ ገንዘብ ፡ አለ ፡ ሲሉ ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡
ባይናቸው ፡ ሳያዩት ፡ የራሳቸው ፡ ገንዘብ ፡ ያደ
ርጉታል ፡ በፊታቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍ
ራት ፡ የለምና ፡ ባይናቸው ፡ በዩት ፡ ጊዜ ፡ በፋቸ
ውም ፡ የበሉት ፡ ይመስላቸዋል ።

መኳንንቶቻቸውም ፡ ያደራ ፡ ገንዘብ ፡ ይበላሉ ፡ ፲፫፤
የሚበሉ ፡ ናቸው ፡ እነሱ ፡ አሉተኞች ፡ ናቸ
ውና ፡ ባንደበታቸውም ፡ የቀና ፡ ነገር ፡ የለምና ፡
ጧት ፡ የተናገሩትን ፡ ማታ ፡ አይደግሙትም ።
የጦም ፡ አዳሪዎችን ፡ የድኆችን ፡ ጩኸት ፡ ቸል ፡ ፲፬፤
ይላሉና ፡ ስደተኞችንም ፡ ከሚቀሟቸው ፡ ከባ
ለጠጎች ፡ እጅ ፡ አድኗቸው ፡ ሰውን ፡ የሚያ
ውኩ ፡ ንጉሦቻቸው ፡ ለክፋት ፡ ይፋጠናሉ ።
የተበደለውንና ፡ ስደተኛውን ፡ ያድኗቸው ፡ ፲፭፤
እንጂ ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ነገሥታቱ ፡ ፍርድን ፡
የሚነፍጉ ፡ አይሁኑ ።
እነሳቸው ፡ ግን ፡ ግብር ፡ የሚያስገብሩ ፡ ናቸው ፡ ፲፮፤
የሰው ፡ ገንዘብ ፡ የሚቀሙ ፡ ናቸው ፡ ወንጀለ
ኞችም ፡ ናቸው ፡ ሥራቸውም ፡ ክፉ ፡ ነውና ፡
እምበሳዩቱ ፡ ከናቷ ፡ ጋራ ፡ ወፍን ፡ ከዕቍላሏ ፡
ጋራ ፡ ሲበሉ ፡ አይራሩም ፡ ያዩትን ፡ የሰሙትን ፡
ሁሉ ፡ የራሳቸው ፡ ገንዘብ ፡ ያደርጋሉ ።
እነሳቸው ፡ ለራሳቸው ፡ ይሰበስቡ ፡ ዘንድ ፡ ይወ ፲፯፤
ዳሉ ፡ እንጂ ፡ ለሕመምተኞችና ፡ ለድኆች ፡
አይራሩም ፡ በግፍ ፡ የሌላውንም ፡ ገንዘብ ፡ ይቀ
ማሉ ፡ በቤታቸው ፡ ያደልቡ ፡ ዘንድ ፡ በሱም ፡
ደስ ፡ ይላቸው ፡ ዘንድ ፡ ያገኙትንም ፡ ሁሉ ፡ ይሰ
በስባሉ ።
ከጕድጓዱ ፡ እንደ ፡ ወጣ ፡ ፍለጋውም ፡ እንደማ ፲፰፤
ይገኝ ፡ ወደ ፡ ቤቱም ፡ እንደማይመለስ ፡ አሸን ፡
ፈጥነው ፡ ይጠፋሉና ፡ በሕይወታቸውም ፡ ሳሉ ፡
በጎ ፡ ሥራን ፡ ስላልሠሩ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተቈ
ጥቶ ፡ በያዛቸው ፡ ጊዜ ፡ ለሰውነታቸው ፡ ወዮ
ላት ።
እግዚአብሔር ፡ ቸል ፡ ባላቸው ፡ ጊዜ ፡ ባንድ ፡ ፲፱፤
መቅሠፍት ፡ እንዳሉ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ይጠፋሉ ፡
ወደ ፡ ንስሐ ፡ ይመለሱ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ብሎ ፡ ይታ
ገሣቸዋል ፡ እንጂ ፡ ፈጥኖ ፡ አያጠፋቸውምና ፡
በሚጠፉበትም ፡ ጊዜ ፡ ይጠፋሉ ።
ወደ ፡ ንስሐ ፡ ባይመለሱ ፡ ግን ፡ ከነሳቸው ፡ አስ ፳፤
ቀድሞ ፡ እንደ ፡ ነበሩ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡
በሚገባ ፡ እንዳልጠበቁ ፡ እንደ ፡ ቀድሞ ፡ ሰዎች ፡
ፈጥኖ ፡ ያጠፉቸዋል ።
የሰው ፡ ሥጋ ፡ የሚበሉ ፡ የሰው ፡ ደም ፡ የሚ ፳፩፤
ጠጡ ፡ ናቸው ፡ ወደ ፡ ኃጢአት ፡ ለመሄድ ፡
ግፍን ፡ ይታጠቃሉና ፡ ይሠራሉና ፡ በፊታቸው ፡
ሁለጊዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ የለም ፡
ከመኝታቸውም ፡ ከተነሡ ፡ በኋላ ፡ ኃጢአት ፡
ለመሥራት ፡ አያርፉም ።
በዚህ ፡ ዓለም ፡ የብዙ ፡ ሰዎች ፡ ሰውነትን ፡ ፳፪፤
ያጠፉ ፡ ዘንድ ፡ ሥራቸውም ፡ መጠጥና ፡ መብል ፡
ወደ ፡ ጥፋትና ፡ ወደ ፡ ኃጢአት ፡ መሄድ ፡ ነው ።

ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

ሥራቸው ፡ ጠማማ ፡ ነውና ፡ ሁሉም ፡ በሚ ፩፤
ያስት ፡ በሰይጣንም ፡ ሥራ ፡ ጸንተው ፡ የሚኖሩ ፡
ናቸውና ፡ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ እግዚአብሔር ፡
ተቈጥቶ ፡ በያዛኋት ፡ ጊዜ ፡ ለሰውነታችሁ ፡ ወዮ
ላት ፡ አለ ።

፪፤ የእግዚአብሔርን ፡ ሥራ ፡ ግን ፡ አያውቁምና ፡
ወደ ፡ ኋላቸው ፡ መልሰውታልና ፡ ሕጌንም ፡
ቸል ፡ ብለዋልና ።
፫፤ እኔም ፡ ኋላ ፡ በፍጻሜ ፡ ዘመን ፡ እንደ ፡ ሥራ
ቸው ፡ ክፋት ፡ መጠን ፡ ፍዳውን ፡ አመጣባቸዋ
ለሁ ፡ ኀጢአታቸው ፡ በኔ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡
ፍርድ ፡ በሚፈረድበት ፡ ቀን ፡ ተበቅዬ ፡ አጠፋ
ቸዋለሁ ፡ የምገድል ፡ የማድን ፡ በመከራ ፡ የም
ገርፍ ፡ ይቅር ፡ የምል ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡
ነኝና ፡ ከሥልጣኔ ፡ አያመልጡምና ።
፬፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከአድማስ ፡ እስከ ፡ አድ
ማስ ፡ ምሉ ፡ ነኝና ፡ ፍጥረቱም ፡ ሁሉ ፡ በሥል
ጣኔ ፡ ተይዟልና ፡ በሰማይና ፡ በምድር ፡ በጥል
ቅና ፡ በባሕርም ፡ ከሥልጣኔ ፡ የሚያመልጥ ፡
የለም ።
፭፤ በምድር ፡ በታች ፡ ያለ ፡ አበብን ፡ አዘዋለሁ ፡
በባሕርም ፡ ውስጥ ፡ ያለ ፡ ዓሣን ፡ አዘዋለሁ ፡
በሰማይ ፡ ያሉ ፡ ወፎችንም ፡ አዛቸዋለሁ ፡
በምድረ ፡ በዳ ፡ ያለ ፡ የበረሃ ፡ አህያውንም ፡
አዘዋለሁ ፡ ከአድማስ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ አድ
ማስ ፡ ድረስ ፡ የኔ ፡ ገንዘብ ፡ ነውና ።
፮፤ በሬቱ ፡ ድንቅ ፡ ሥራን ፡ የምሠራ ፡ ታምራትን ፡
የማደርግ ፡ እኔ ፡ ነኝና ፡ በምድርና ፡ በሰማይ ፡
ከሥልጣኔ ፡ የሚያመልጥ ፡ የለም ፡ ወዴት ፡ ትሄ
ዳለህ ፡ ምንስ ፡ ትሠራለህ ፡ የሚለኝ ፡ የለም ።
፯፤ እኔም ፡ በመላእክት ፡ አለቆችና ፡ ሠራዊት ፡
ላይ ፡ አዛለሁ ፡ ስሙ ፡ የሚጠራው ፡ ሁሉ ፡
ፍጥረት ፡ የኔ ፡ ገንዘብ ፡ ነው ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡
ያሉ ፡ አውሬዎችና ፡ በሰማይ ፡ ያሉ ፡ ወፎችም ፡
ሁሉ ፡ ከብቶችም ፡ የኔ ፡ ገንዘቦች ፡ ናቸው ።
፰፤ ከእዜብ ፡ ነፋስ ፡ ይነሣል ፡ በመስዕም ፡ ያለ ፡
ድርቅ ፡ ይጸናል ፡ ኋላ ፡ በፍጻሜ ፡ ዘመን ፡ ወደሷ ፡
የሚመጣ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ መፈራት ፡ ገናንነ
ትም ፡ የተነሣ ፡ የኤርትራ ፡ ባሕር ፡ ተሰምታ ፡
ትጠፋለች ።
፱፤ እሱ ፡ የሞቱትንና ፡ ያሉትን ፡ ሰዎች ፡ ይገዛልና ፡
ከሳባና ፡ ከኖባ ፡ ከሕንደኬና ፡ ከኢትዮጵያም ፡
ወሰናቸውና ፡ አውራጃቸውም ፡ ጋራ ፡ ሁሉ ፡
ተሰምታ ፡ ትጠፋለች ።
፲፤ ከፍ ፡ ባለ ፡ ሥልጣንም ፡ በየዋህነት ፡ ሁሉን ፡
ይጠብቃል ፡ ከሥልጣኑ ፡ ሁሉ ፡ የሱ ፡ ሥልጣን ፡
ይበልጣልና ፡ በሥልጣኑም ፡ ምዕመናንን ፡ ይጠ
ብቃል ።
፲፩፤ ሥልጣኑም ፡ ከሥልጣኑ ፡ ሁሉ ፡ ይጸናልና ፡
መንግሥቱም ፡ ከመንግሥቱ ፡ ሁሉ ፡ ይበልጣ
ልና ፡ ሥልጣኑም ፡ ዓለሙን ፡ ሁሉ ፡ የሚገዛ ፡
ነውና ፡ ሁሉን ፡ ይችላልና ፡ የሚሳነውም ፡ የለ
ምና ።
፲፪፤ በሰማይ ፡ ያሉ ፡ ደመናዎችን ፡ ሁሉ ፡ ይገዛል ፡
በምድር ፡ ላሉ ፡ ከብቶች ፡ ሣርን ፡ ያበቅላል ፡
በዠርገዥሩም ፡ ላይ ፡ ፍሬን ፡ ይሰጣል ።
፲፫፤ እንደ ፡ ወደደ ፡ ለሁሉ ፡ በየወገኑ ፡ ይመግባል ፡
በየፍሬው ፡ በየምግቡም ፡ የፈጠረውን ፡ ሁሉ ፡
ይመግባል ፡ ለገብረ ፡ ጉንዳንም ፡ በምድር ፡
በታች ፡ ላሉ ፡ ለኩኩባንም ፡ በምድር ፡ ላይ ፡
ላሉ ፡ ከብቶችም ፡ ለአውሬዎችም ፡ ይመግባቸ
ዋል ፡ ለጻለየ ፡ ሰውም ፡ ጸሎቱን ፡ ይሰጠዋል ፡
እናት ፡ አባቱ ፡ የሞቱበት ፡ ልጅንና ፡ በሌቱቶ
ችንም ፡ ልመናቸውን ፡ ቸል ፡ አይልም ።
የክፉ ፡ ሰዎች ፡ አመፃቸው ፡ እንደ ፡ ጥቅል ፡ ፲፬፤
ነፋስ ፡ የበደለኞች ፡ ጉባኤያቸውም ፡ እንደ ፡
ጉም ፡ ሽንት ፡ ነውና ፡ ይልቁንም ፡ በየጊዜው ፡
ወደሱ ፡ የሚለምኑ ፡ የንጹሐንን ፡ ልመና ፡ ይቀ
በላል ።
ሰውነታቸውም ፡ እንደምትበር ፡ ወፍ ፡ ነውና ፡ ፲፭፤
የብርና ፡ የወርቅ ፡ የሚሆን ፡ የመልክቸውም ፡
ደም ፡ ግብት ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ጠፊ ፡ ነውና ፡ የእ
ግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ የዘነጉ ፡ ሰዎች ፡ መመር
መሪያቸው ፡ እንጂ ፡ ወርቃቸው ፡ አይጠቅማቸ
ውም ፡ ልብሳቸውንም ፡ ብል ፡ ይበላዋል ።
የስንዴውንና ፡ የገብሱንም ፡ ድልብ ፡ ፈጽሞ ፡ ፲፮፤
ነቀዝ ፡ ይበላዋል ፡ ሁሉም ፡ ትናንትና ፡ እንዳለ
ፈችቱ ፡ ቀን ፡ ያልፋል ፡ ከፍ ፡ የወጣ ፡ ቃልም ፡
እንዳይመለስ ፡ የኀጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ ገንዘ
ብም ፡ እንደሱ ፡ ነው ፡ ያማረ ፡ አኗኗራቸውም ፡
እንደሚያልፍ ፡ ጥላ ፡ ነው ፡ የኀጢአተኞች ፡
ሰዎች ፡ ገንዘባቸው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
እንደ ፡ ውሰት ፡ ልብስ ፡ ነው ።
ለድኃ ፡ እየራሩ ፡ ክብረዋልና ፡ የጦም ፡ አዳሪዎ ፡ ፲፯፤
ችንና ፡ እናት ፡ አባቱ ፡ የሞቱበት ፡ ልጅ ፡ ፍር
ድን ፡ ይሰማሉና ፡ ደጋግ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ቢከ
ብሩ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቸል ፡ አይላቸውም ፡ ከቤ
ታቸው ፡ ልጆች ፡ ቸል ፡ ሳይሉ ፡ ለስደተኛው ፡
ለጦም ፡ አዳሪው ፡ ይሰጡ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ከሰጣቸው ፡ ልብስ ፡ ለተራቆቱ ፡ እያለ
በሱ ፡ ያከብረዋልና ፡ እግዚአብሔር ፡ አይላቸ
ውም ።
የታመኑ ፡ ሰዎችን ፡ ፍርድ ፡ አያደሉም ፡ የምን ፡ ፲፰፤
ደኞችንም ፡ ደመወዝ ፡ አያሳድሩም ፡ የእግዚአ
ብሔር ፡ ነገር ፡ አፉ ፡ ሁለት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ሰይፍ ፡
እውነት ፡ ነውና ፡ የከበረ ፡ ነውና ፡ በወራቶቻ
ቸው ፡ ቍጥር ፡ በሚዛናቸው ፡ ልክ ፡ በደልን ፡
አያደርጉም ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፮ ።

ድሆች ፡ ግን ፡ ዳግመኛ ፡ በመኝታቸው ፡ ያስ ፩፤
ባሉ ፡ ባለ ፡ ጠጎች ፡ ባይቀበሏቸው ፡ ግን ፡ ልም
ላሜ ፡ እንደሌለው ፡ እንደ ፡ ደረቅ ፡ እንጨት ፡
ይሆናሉ ፡ ርጥበትም ፡ ከሌለ ፡ ዘንድ ፡ ሥር ፡ አይ
ለመልምም ፡ ሥርም ፡ ከሌለ ፡ ቅጠሉ ፡ አይለመ
ልምም ።
ቅጠል ፡ ለፍሬ ፡ ጌጥ ፡ ለሚሆን ፡ አበባ ፡ ያገለግ ፪፤
ላልና ፡ ቅጠሉ ፡ ከልለመለመ ፡ ፍሬ ፡ አያፈራም ፡
የሰው ፡ ፍጻሜው ፡ ሃይማኖት ፡ ነውና ፡ ሃይማ
ኖት ፡ ለሌለው ፡ ሰው ፡ ምግባር ፡ የለውም ።
ሃይማኖትን ፡ ከጸና ፡ ምግባርን ፡ ሠራ ፡ እግዚአ ፫፤
ብሔርም ፡ እውነትን ፡ የቀና ፡ ሥራን ፡ በሚሠራ ፡
ሰው ፡ ደስ ፡ ይለዋል ።

፬፤ ለለመነውም ፡ ሰው ፡ የልመናውን ፡ ያንደበቱ
ንም ፡ ዋጋ ፡ ይሰጠዋል ፡ እውነተኛውንም ፡ ሰው ፡
ስለ ፡ ሠራው ፡ እውነተኛ ፡ ሥራው ፡ አይበድ
ለውም ።
፭፤ እግዚአብሔር ፡ እውነተኛ ፡ ነውና ፡ እውነት ፡
ነገርን ፡ ወዷልና ፡ ኃጢአተኛውን ፡ ሰው ፡ ስለ ፡
ሠራው ፡ ሥራ ፡ ክፋት ፡ ያለ ፡ ንስሐ ፡ አያጸድቀ
ውም ፡ ምድርና ፡ ሰማይን ፡ የሚገዛ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡
የሰውም ፡ ሁሉ ፡ ነፍስ ፡ በሥልጣኑ ፡ ተይዟ
ልና ፡ በፍርድ ፡ጊዜ ፡ ከድኃው ፡ ለባለጠጋው ፡
አያደላምና ፡ ያለ ፡ ንስሐ ፡ አያጸድቀውም ።

ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

፩፤ ዓለሙን ፡ ሁሉ ፡ ከለ ፡ መኖር ፡ ወደ ፡ መኖር ፡
አምጥቶ ፡ ፈጠረ ፡ ኮረብቶችንና ፡ ተራሮችንም ፡
ፈጽሞ ፡ አዘጋጀ ፡ ምድርንም ፡ በውኃ ፡ ላይ ፡
አጸናት ፡ በሕርም ፡ እንዳትንቀጠቀጥ ፡ በሸዋ ፡ ወሰ
ናት ፡ እግዚአብሔር ፡ በመጀመሪያ ፡ ቃሉ ፡ ብር
ሃን ፡ ይፈጠር ፡ ብሏልና ።
፪፤ ይህ ፡ ዓለም ፡ በጨለማ ፡ ተሸፍኖ ፡ ሳለ ፡ ብርሃን ፡
ተፈጠረ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፍጥረቱን ፡ ሁሉ ፡
ፈጠረ ፡ ይኸንንም ፡ ዓለም ፡ አዘጋጀ ፡ በሚገ
ባም ፡ በሚቀናም ፡ ገንዘብ ፡ ይችን ፡ ዓለም ፡ አጸ
ናት ፡ ምሺት ፡ ጨለማ ፡ ይሁን ፡ አለ ።
፫፤ ዳግመኛም ፡ እግዚአብሔር ፡ ብርሃን ፡ ይፈጠር ፡
አለ ፡ ነጋ ፡ ብርሃንም ፡ ሆነ ፡ የላይኛውንም ፡ ውኃ ፡
ወደ ፡ ሰማይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረገው ።
፬፤ እንደ ፡ ድንኳንም ፡ ዘረጋው ፡ በነፋስም ፡ አጸ
ናው ፡ የታችኛውንም ፡ ውኃ ፡ በጕድጓድ ፡
ውስጥ ፡ አኖረው ።
፭፤ የባሕሩንም ፡ ቍልፍ ፡ በሸዋ ፡ ዘጋው ፡ በውኃ
ውም ፡ እንዳይሰጥሙ ፡ በሥልጣኑ ፡ አጸናቸው ፡
እንስሳትንና ፡ አራዊትንም ፡ በውስጧ ፡ አኖ
ራቸው ፡ ታላላቆች ፡ አውሬዎች ፡ የሆኑ ፡ ሌዋ
ታንና ፡ ብሔሞትንም ፡ በውስጧ ፡ አኖራቸው ፡
ቍጥር ፡ የሌላቸው ፡ የሚታዩት ፡ የማይታዩት ፡
አውሬዎችንም ፡ በውስጡ ፡ አኖራቸው ።
፮፤ በሦስተኛው ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ በምድር ፡
ላይ ፡ አትክልትን ፡ ሥሩን ፡ ሁሉ ፡ እንጨቶች
ንም ፡ በየወገናቸው ፡ የሚያፈሩ ፡ ፍሬዎችንም ፡
ሊያዩት ፡ ያማረ ፡ የደጓንነት ፡ እንጨትንም ፡
ፈጠረ ።
፯፤ ሊያዩትም ፡ ያማረ ፡ ሊበሉትም ፡ የጣፈጠ ፡ የደ
ጓንነት ፡ እንጨትንም ፡ ፈጠረ ፡ ሣርንም ፡ ዘሩ ፡
ከውስጡ ፡ የሚገኝ ፡ ተክልንም ፡ ሁሉ ፡ ለወፎ
ችና ፡ ለከብቶች ፡ ላውሬዎችም ፡ መብል ፡ ሊሆን ፡
ፈጠረ ፡ ለፈጠረውም ፡ ሁሉ ፡ ምግብን ፡ ሰጠ ።
፰፤ መሸ ፡ ነጋ ፡ ባራተኛዪቱም ፡ ቀን ፡ ጠፈር ፡ በሚ
ባል ፡ ሰማይ ፡ ብርሃን ፡ ይፈጠር ፡ አለ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ጨረቃና ፡ ፀሐይን ፡ ከዋክብትንም ፡
ፈጥሮ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ያበሩ ፡ ዘንድ ፡ መዓል
ትና ፡ ሌሊትንም ፡ ይመግቧቸው ፡ ዘንድ ፡ ጠፈር ፡
በሚባል ፡ ሰማይ ፡ አኖራቸው ።
፱፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ጨረቃና ፡ ፀሐይ ፡ ከዋክብትም ፡
በሌሊትና ፡ በመዓልትም ፡ ተፈራረቁ ።
በምስተኛዪቱም ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ በውኃ ፡ ፲፤
ውስጥ ፡ የሚኖሩ ፡ እንስሳና ፡ አውሬዎችን ፡
ሁሉ ፡ በሰማይ ፡ ላይ ፡ የሚበሩ ፡ ወፎችንም ፡
ሁሉ ፡ የሚታየውንና ፡ የማይታየውን ፡ ሁሉ ፡
ይኸንን ፡ ሁሉ ፡ ፈጠረ ።
በስድስተኛዪቱም ፡ ቀን ፡ ከብቶችንና ፡ አውሬ ፲፩፤
ዎችን ፡ ሌሎችንም ፡ ፈጠረ ፡ ሁሉንም ፡ ፈጥሮ ፡
አዘጋጅቶ ፡ አዳምን ፡ በምሳሌውና ፡ በመልኩ ፡
ፈጠረው ።
የፈጠራቸው ፡ እንስሳትና ፡ አውሬዎችን ፡ ሁሉ ፡ ፲፪፤
ይነግሥባቸው ፡ ዘንድ ፡ ሰጠው ፡ ዳግመኛም ፡
እንስሳትንና ፡ አራዊትን ፡ ሁሉ ፡ ዓሣዎችንም ፡
ሁሉ ፡ በባሕር ፡ ያሉ ፡ ሌዋታንና ፡ ብሔሞትንም ።
በዚህ ፡ ዓለም ፡ የሚኖሩ ፡ ላሞችን ፡ ሁሉና ፡ ፲፫፤
በጎችንም ፡ የማይታየውንና ፡ የሚታየውን ፡
እንስሳ ፡ ሰጠው ።
በምሳሌውና ፡ በመልኩ ፡ የፈጠረው ፡ አዳም ፲፬፤
ንም ፡ በገነት ፡ አኖረው ፡ ይበላ ፡ ዘንድ ፡ ተክል
ንም ፡ ይኰትኵታት ፡ ዘንድ ፡ በዚያም ፡ እግዚአ
ብሔርን ፡ ያመሰግነው ፡ ዘንድ ።
ትእዛዙንም ፡ እንዳያፈርስ ፡ ከዚህ ፡ ከዕፀ ፡ በለስ ፡ ፲፭፤
በበላችሁበት ፡ ጊዜ ፡ ሞትን ፡ ትሞታላችሁ ፡
ብሏልና ።
ሞትን ፡ ከሚያመጣ ፡ ክፋና ፡ በጎን ፡ ልብ ፡ ከሚያ ፲፮፤
ስደርግ ፡ ሞትን ፡ ከሚያመጣ ፡ ከዕፀ ፡ በለስም ፡
እንዳይበላ ፡ አዘዘው ።
እናታችን ፡ ሔዋን ፡ በእባብ ፡ ማሳት ፡ ተሸንግላ ፡ ፲፯፤
ከዚያ ፡ ከዕፀ ፡ በለስ ፡ በልታ ፡ ላባታችን ፡ ለአ
ዳም ፡ ሰጠችው ።
አዳምም ፡ ከዚያ ፡ ከዕፀ ፡ በለስ ፡ በልቶ ፡ በልጆ ፲፰፤
ቹና ፡ በራሱ ፡ ሞትን ፡ አመጣ ።
ትእዛዙን ፡ አፍርሷልና ፡ እግዚአብሔር ፡ ከርሷ ፡ ፲፱፤
አትብላ ፡ ብሎ ፡ ከዘዘው ፡ ከዚያም ፡ ከዕፀ ፡ በለስ ፡
በልቷልና ፡ እግዚአብሔር ፡ በአባታችን ፡ በአ
ዳም ፡ ተቈጣ ፡ ከገነትም ፡ አስወጥቶ ፡ ሰደደው ፡
ያርሳት ፡ ዘንድ ፡ ጽሮ ፡ ግሮም ፡ የድካሙን ፡
ዋጋ ፡ ይበላ ፡ ዘንድ ፡ ትእዛዙን ፡ በፈረሰ ፡ ጊዜ ፡
ስለሱ ፡ የረገማት ፡ አሚከላና ፡ እሾህን ፡ የምታ
በቅል ፡ ያችንም ፡ ምድር ፡ ሰጠው ።
እግዚአብሔርም ፡ ወደዚች ፡ ምድር ፡ በወጣው ፡ ፳፤
ጊዜ ፡ አዳም ፡ ወደ ፡ ፍጹም ፡ ኀዘን ፡ ተመለሰ ፡
ምድርንም ፡ ያርሳት ፡ ዘንድ ፡ ጽሮ ፡ ግሮም ፡
በድካምና ፡ በትዕግልትም ፡ ይበላ ፡ ጀመር ።

ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

ልጆቹም ፡ በዝተው ፡ ከኖሩ ፡ በኋላ ፡ ከነርሳ ፩፤
ቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚያመሰግኑት ፡ የሚ
ያከብሩት ፡ ትእዛዙንም ፡ የማያፈርሱ ፡ ነበሩ ።
የተደረገውን ፡ እንግዲህም ፡ የሚደረገውን ፡ ፪፤
የሚናገሩ ፡ ነቢያት ፡ ነበሩ ፡ ከልጆቹም ፡ ሐሰት ፡
የሚናገሩ ፡ ሰውንም ፡ የሚበድሉ ፡ ኃጢአተ
ኞች ፡ ነበሩ ፡ የአዳም ፡ የበክር ፡ ልጁ ፡ ቃየል ፡
ክፉ ፡ ሆነ ፡ ወንድሙ ፡ አቤልንም ፡ ገደለው ።

፫፤ ወንድሙን ፡ አቤልን ፡ ስለ ፡ ገደለ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ በቃየል ፡ ፍርድን ፡ ፈረደ ፡ ደሙንም ፡
ስለ ፡ ጠጣች ፡ እግዚአብሔር ፡ ምድርን ፡ ተቈ
ጣት ።
፬፤ እግዚአብሔርም ፡ ቃየልን ፡ ወንድምሀ ፡ አቤል ፡
ወዴት ፡ አለ ፡ አለው ፡ ቃየልም ፡ በልቡ ፡ ትዕ
ቢት ፡ የወንድሜ ፡ የአቤል ፡ ጠባቂ ፡ እኔ ፡ ነኝን ፡
አለ ።
፭፤ አቤል ፡ ንጹሕ ፡ ሰውን ፡ ሆነ ፡ ቃየል ፡ ግን ፡ ደግ ፡
ሰው ፡ ወንድሙ ፡ አቤልን ፡ በመግደል ፡ ኃጢአ
ተኛን ፡ ሆነ ።
፮፤ ዳግመኛ ፡ ደግ ፡ ልጅ ፡ ሴት ፡ ተወለደ ፡ አዳም ፡
ስድሳ ፡ ልጆችን ፡ ወለደ ፡ ከነሳቸው ፡ ደጋጎች ፡
ሰዎች ፡ ክፉዎች ፡ ሰዎች ፡ አሉ ።
፯፤ ከነሳቸውም ፡ ደጋጎች ፡ ሰዎች ፡ አሉ ፡ ነቢያት ፡
የሆኑ ፡ ከጻድቃንና ፡ ኃጢአተኞች ፡ የሆኑ ፡ ሰዎ
ችም ፡ አሉ ።
፰፤ ደጋግ ፡ ሰዎች ፡ የሆኑ ፡ የአባታቸው ፡ የአዳምን ፡
ፈቃድ ፡ ከአዳም ፡ ጀምሮ ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ሕግ ፡ እስከ ፡ ጠበቀ ፡ ደግ ፡ ሰው ፡ እስከሚሆን ፡
እስከ ፡ ኖኅ ፡ ድረስ ፡ ለልጁ ፡ ለሴት ፡ የነገረው
ንም ፡ ሁሉ ፡ የሚፈጽሙ ፡ የተመረጡ ፡ ሰዎች ፡
አሉ ።
፱፤ እሱም ፡ ለልጆቹ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ አስ
ጠበቃቸው ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ እንዳያ
ፈርሱ ፡ አባታቸው ፡ ኖኅ ፡ እንደ ፡ ነገራቸው ፡
እነሳቸውም ፡ ለልጆቻቸው ፡ ይነግሩ ፡ ዘንድ ፡
የእግዚአብሔርንም ፡ ሕግ ፡ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ፡
ጠብቁ ፡ አላቸው ።
፲፤ እነሳቸውም ፡ ከነሳቸው ፡ በኋላ ፡ ለተወለዱ ፡
ሰዎች ፡ ለልጆቻቸው ፡ እያስተማሯቸው ፡ ኖሩ ።
፲፩፤ ሰይጣን ፡ ግን ፡ አባቶቻቸውን ፡ ለመቃብር ፡ በደ
ረሱ ፡ ሥሰል ፡ በለበቸው ፡ ጣዖታት ፡ አድሮ ፡
እሺ ፡ የሚሉትን ፡ ሰዎች ፡ ድል ፡ ነሥቶ ፡ ሲናገራ
ቸው ፡ ኖረ ፡ እነሳቸውም ፡ የኃጢአት ፡ መምር ፡
የሚሆን ፡ ዲያብሎስ ፡ ያዘዛቸውን ፡ ሁሉ ፡ ሲያ
ደርጉ ።
፲፪፤ የእግዚአብሔርን ፡ ፈቃድ ፡ የሚፈጽም ፡ ደግ ፡
ሰው ፡ አብርሃም ፡ እስኪነሣ ፡ ድረስ ፡ እንደ ፡
ሥርዓታቸው ፡ ጣዖታቱንም ፡ ሲያመልኩ ፡ ኖሩ ።
፲፫፤ ከዘመዶቹ ፡ ተለይቶ ፡ አስቀድሞ ፡ በሕጉ ፡ ጸንቶ ፡
ኖረልና ፡ እግዚአብሔርም ፡ በነፋስና ፡ በእሳት ፡
አድሮ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ መሐላን ፡ ተማማለ ።
፲፬፤ ለሱ ፡ ምድረ ፡ ርስትን ፡ ይሰጠው ፡ ዘንድ ፡ ለል
ጆቹም ፡ እስከ ፡ ዘለዓለሙ ፡ ድረስ ፡ ይሰጣቸው ፡
ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ማለለት ።
፲፭፤ ያባቱ ፡ የአብርሃምን ፡ ርስት ፡ ይሰጠው ፡ ዘንድ ፡
ለይስሐቅም ፡ እንደሱ ፡ ማለለት ፡ ያባቱ ፡ የይስ
ሐቅን ፡ ርስት ፡ ይሰጠው ፡ ዘንድ ፡ ለያዕቆብም ፡
ማለለት ፡ እንደ ፡ ይስሐቅ ፡ ማለለት ።
፲፮፤ ከነሳቸውም ፡ በኋላ ፡ ከያዕቆብ ፡ የተወለዱ ፡
ልጆቻቸውን ፡ ከሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ነገደ ፡ እስራ
ኤል ፡ ለይቶ ፡ ክህናትንና ፡ ነገሥታትን ፡ አደረ
ጋቸው ፡ ብዙ ፡ ፈጽማችሁም ፡ የብዙ ፡ ብዙ ፡
ሁኑ ፡ ብሎ ፡ መረቃቸው ።
የአባቶቻቸውንም ፡ ርስት ፡ ሰጣቸው ፡ ነገር ፡ ፲፯፤
ግን ፡ እየመገባቸው ፡ እየወደዳቸው ፡ እግዚአ
ብሔርን ፡ ማሳዘን ፡ በሁሉም ፡ አልተዉም ።
በጠፋቸውም ፡ ጊዜ ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ በአምልኮ ፡ ፲፰፤
ይፈልጉታል ፡ ከኃጢአትም ፡ ተመልሰው ፡ ወደ ፡
እግዚአብሔር ፡ ይሄዳሉ ፡ ይወዳቸዋልና ፡ እግ
ዚአብሔርም ፡ ይቅር ፡ ይላቸዋል ።
የፈጠረውን ፡ ሁሉ ፡ ራርቶ ፡ ይቅር ፡ ይላልና ፡ ፲፱፤
የሚወዳቸውም ፡ ስለ ፡ አባቶቻቸው ፡ ሥራ ፡
ነው ፡ እንጂ ፡ ስለ ፡ ራሳቸው ፡ ሥራ ፡ አይደለም ።
የተራቡትን ፡ ሰውነትን ፡ ያጠግብ ፡ ዘንድ ፡ በበረ ፳፤
ከትም ፡ ቀኝ ፡ እጁን ፡ ይዘረጋል ፡ ሰምግብ ፡ እህ
ልን ፡ ያበዛ ፡ ዘንድ ፡ ይቅር ፡ ለማለትም ፡ ዓይኑን ፡
ይገልጣል ።
ለቍራዎች ፡ ጫጩቶች ፡ ለሚለምኑት ፡ ለአው ፳፩፤
ሬዎችም ፡ ምግብ ፡ ይሰጣቸዋል ፡ ወደርሱ ፡
በጮሁ ፡ ጊዜ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ከጊዜው ፡
ከዘገዩት ፡ ጠላቶቻቸው ፡ እጅ ፡ ያድናቸዋል ።
ያሳዘኑት ፡ ዘንድ ፡ ዳግመኛም ፡ ወደ ፡ ኃጢአት ፡ ፳፪፤
ይመለሳሉ ፡ እርሱም ፡ በዙሪያቸው ፡ ያሉ ፡ ጠላ
ቶቻቸውን ፡ አሕዛብን ፡ ያስነሣባቸዋል ፡ ያጠፏ
ቸዋል ፡ ይገድሏቸዋል ፡ ይማርኳቸዋል ።
ዳግመኛም ፡ በልቅሶና ፡ በኀዘን ፡ ወደ ፡ እግዚ ፳፫፤
አብሔር ፡ ይጮኻሉ ፡ እሱም ፡ ረዳትን ፡ ልኮ ፡
በነቢያት ፡ እጅ ፡ እነሳቸውን ፡ ያዳነበት ፡ ጊዜ ፡
አለ ።
በመሳፍንትም ፡ እጅ ፡ ያዳነበት ፡ ጊዜ ፡ አለ ፡ እግ ፳፬፤
ዚአብሔርም ፡ በሳዘኑት ፡ ጊዜ ፡ ጠላቶቻቸው ፡
አስገበሯቸው ፡ ማረኳቸው ።
ዳዊትም ፡ ተነሥቶ ፡ ከኢሎፍላውያን ፡ እጅ ፡ ፳፭፤
አዳናቸው ፤ ዳግመኛም ፡ እግዚአብሔርን ፡ አሳ
ዘኑት ፡ እግዚአብሔርም ፡ የሚያስጨንቋቸው ፡
አሕዛብን ፡ አስነሣባቸው ።
በዮፍታሔም ፡ እጅ ፡ እነሳቸውን ፡ ያዳነበት ፡ ፳፮፤
ጊዜ ፡ አለ ፡ ዳግመኛም ፡ በመከራቸው ፡ ጊዜ ፡
ያዳናቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ዘነጉት ። እግዚአ
ብሔር ፡ ፍዳውን ፡ አምጥቶባቸዋልና ፡ ክፉ ፡
የሆኑ ፡ መከራ ፡ የሚያጸኑባቸውን ፡ ፈጽመውም ፡
የሚማርኳቸውን ፡ ጠላቶችን ፡ ያስነሣባቸዋል ።
በመከራ ፡ በተጨነቁ ፡ ጊዜ ፡ ተይዘውም ፡ ዳግ ፳፯፤
መኛ ፡ ወደሱ ፡ ጮሁ ፡ እሱም ፡ በጌዴዎን ፡ እጅ ፡
አዳናቸው ፡ ዳግመኛም ፡ በእጃቸው ፡ ሥራ ፡ እግ
ዚአብሔርን ፡ አሳዘኑት ።
እሱም ፡ ዳግመኛ ፡ መከራ ፡ የሚያጸኑባቸውን ፡ ፳፰፤
አሕዛብ ፡ አስነሣባቸው ፡ ተመልሰውም ፡ ወደ ፡
እግዚአብሔር ፡ አለቀሱ ፡ ጮሁ ።
ዳግመኛም ፡ በሶምሶን ፡ እጅ ፡ ከአሕዛብ ፡ አዳና ፳፱፤
ቸው ፡ ከመከራውም ፡ ጥቂት ፡ አረፉ ። በቀደመ
ውም ፡ ኃጢአታቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያሳዝ
ኑት ፡ ዘንድ ፡ ተነሡ ።
እሱም ፡ ዳግመኛ ፡ የሚያስጨንቋቸው ፡ ሌሎች ፡ ፴፤
አሕዛብን ፡ አስነሣባቸው ፡ ዳግመኛም ፡ ረዳትን ፡
ይሰድላቸው ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡

ጮሁ ፡ አለቀሱ ፡ በባርቅና ፡ በዲቦራም ፡ እጅ ፡
ከአሕዛብ ፡ አዳናቸው ።
፲፩ ዳግመኛ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እያመለኩት ፡
ጥቂት ፡ ወራት ፡ ኖሩ ፡ ዳግመኛም ፡ በቀደመው ፡
ኃጢአታቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ዘንጉት ፡ አሳ
ዘኑት ።
፲፪ እሱም ፡ የሚያስጨንቋቸው ፡ ሌሎች ፡ አሕዛ
ብን ፡ አስነሣባቸው ፡ ዳግመኛም ፡ በዮዲት ፡
እጅ ፡ አዳናቸው ፤ ዳግመኛም ፡ ጥቂት ፡ ወራት ፡
ተቀምጠው ፡ እንደ ፡ ቀደመው ፡ እግዚአብ
ሔርን ፡ በኃጢአታቸው ፡ ያሳዝኑት ፡ ዘንድ ፡
ተነሡ ።
፲፫ እሱም ፡ የሚገዟቸው ፡ አሕዛብን ፡ አስነሣባቸው ፡
እነሳቸውም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮሁ ፡ አለ
ቀሱ ፤ የይሁዳን ፡ አገር ፡ ይወጋ ፡ ዘንድ ፡ የመጣ ፡
አርበኛ ፡ የሆን ፡ አቤሜሌክን ፡ ራሱን ፡ መትቶ
ታልና ።
፲፬ በዙሪያው ፡ ባሉ ፡ በልጆቹና ፡ በማታትዩም ፡
እጅ ፡ አዳናቸው ፡ ያም ፡ አርበኛ ፡ በሞተ ፡ ጊዜ ፡
ሠራዊቱ ፡ ሸሹ ፡ ተበተኑ ፡ የእስራኤልም ፡
ልጆች ፡ እስከ ፡ ኢያቦቅ ፡ ድረስ ፡ ተከትለው ፡
ወጓቸው ፡ ከነሳቸውም ፡ አንድ ፡ ሰውን ፡ ስንኳ ፡
አላስቀሩም ።
፲፭ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ጥቂት ፡ ቈይተው ፡ እግዚአብሔ
ርን ፡ ያሳዝኑት ፡ ዘንድ ፡ ተነሡ ፡ እሱም ፡ የሚገዟ
ቸው ፡ አሕዛብን ፡ አስነሣባቸው ፡ ዳግመኛም ፡ ፈጽ
መው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮሁ ፤ እግዚአ
ብሔርን ፡ ሁለጊዜ ፡ አሳዝነውታልና ፡ ሕጉንም ፡
አፍርሰዋልና ፡ እግዚአብሔርም ፡ ጩኸታቸ
ውንና ፡ ልቅሷቸውን ፡ ቸል ፡ አለ ።
፲፮ ማርከውም ፡ ከካህናቶቻቸው ፡ ጋራ ፡ ወደባቢ
ሎን ፡ ሰዎች ፡ አገር ፡ ወሰዷቸው ።
፲፯ ከዚያም ፡ ኃጢአትን ፡ እየሠሩ ፡ ጣዖትንም ፡
እያመለኩ ፡ ከዳተኞች ፡ የሆኑ ፡ የእስራኤል ፡
ልጆች ፡ እግዚአብሔርን ፡ ማሳዘን ፡ አልተዉም ።
፲፰ እግዚአብሔር ፡ በዚያ ፡ በኃጢአታቸው ፡ አንድ ፡
ጊዜ ፡ ያጠፉቸው ፡ ዘንድ ፡ ተቈጣ ፡ ሐማ ፡ በን
ጉሡ ፡ ማጥን ፡ እልፍ ፡ ወርቅን ፡ አግብቶ ፡ በታ
ወቀበት ፡ ቀን ፡ ያጠፉቸው ፡ ዘንድ ፡ በነገረው ፡
ጊዜ ፡ ከሕንደኬ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ኢትዮጵያም ፡
ድረስ ፡ በፋርስ ፡ አገር ፡ ልጆቻቸውን ፡ እንዳያ
ስቀር ፡ በንጉሡ ፡ በአርጤክስስ ፡ ልቡና ፡ ቍጣን ፡
አሳደረ ።
፲፱ እንዲህ ፡ አደረገ ፡ በንጉሡም ፡ ሥልጣን ፡ መል
ክት ፡ የተጻፈበትን ፡ ደብዳቤ ፡ ጻፈ ፡ ወደፋር
ስም ፡ አገር ፡ ያደርስ ፡ ዘንድ ፡ በእጁ ፡ ያለ ፡ ማኅ
ተምን ፡ ሰጠው ።
፳ ንጉሥ ፡ እንዳዘዘ ፡ ሊያጠፏቸው ፡ በወደደበት ፡
በንዲት ፡ ቀን ፡ ያጠፉቸው ፡ ዘንድ ፡ ማኅተምን ፡
ሰጠው ፡ ገንዘባቸው ፡ ወርቁን ፡ ብሩን ፡ ግን ፡
ወደንጉሡ ፡ ማጥን ፡ ያገቡ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ።
፳፩ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ይህንን ፡ ነገር ፡ በሰሙ ፡
ጊዜ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፈጽመው ፡ ጮሁ ፡
አለቀሱ ፡ ለመርዶክዮስም ፡ ነገሩት ፡ መርዶክዮ
ስም ፡ ለአስቴር ፡ ነገራት ።
አስቴርም ፡ ጾሙ ፡ ለምኑ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ፳፪
ወገኖችም ፡ ሁሉ ፡ ባላችሁበት ፡ ቦታ ፡ ወደ ፡
እግዚአብሔር ፡ ጩሁ ፡ አለች ።
መርዶክዮስም ፡ ማቅ ፡ ለበሰ ፡ በራሱም ፡ ትቢ ፳፫
ያን ፡ ነሰነሰ ፡ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ ባሉበት ፡
አገር ፡ ጾሙ ፡ ለመኑ ፡ ንስሐ ፡ ገቡ ።
አስቴርም ፡ ፈጽማ ፡ አዘነች ፡ ንግሥትም ፡ ሁና ፡ ፳፬
ማቅ ፡ ለበሰች ፡ ትቢያን ፡ ነሰነሰች ፡ ራሷንም ፡
ተላጨች ፡ የፋርስም ፡ ንግሥታት ፡ ሽቱን ፡ እን
ዲቀቡ ፡ ሽቱን ፡ አልተቀባችም ፡ በጥልቅ ፡ ልቡ
ናዋም ፡ ወደ ፡ አባቶቿ ፡ ፈጣሪ ፡ ወደ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ጮኸች ፡ አለቀሰች ።
ስለዚህም ፡ ነገር ፡ በፋርስ ፡ ንጉሥ ፡ በአርጤክ ፳፭
ስስ ፡ ዘንድ ፡ መወደድን ፡ ሰጣት ፡ ላባቶቿም ፡
ፈጣሪ ፡ ደግ ፡ ምሳን ፡ አደረገች ።
ሐማና ፡ ንጉሡም ፡ አስቴር ፡ ወደ ፡ አዘጋጀችው ፡ ፳፮
ምሳ ፡ ገቡ ፡ በመርዶክዮስም ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡
እንደወደደ ፡ እግዚአብሔር ፡ በዚያ ፡ ሐማን ፡
ፍዳውን ፡ ከፈለው ፡ በረጅም ፡ እንጨት ፡ ላይም ፡
ሰቀሉት ።
በፊቃዳቸው ፡ ሁሉ ፡ እንዳሉ ፡ እስራኤልን ፡ ፳፯
ይተዋቸው ፡ ዘንድ ፡ እንዳያስገብሯቸውም ፡
እንዳይቀሟቸውም ፡ እንዳይበድሏቸውም ፡ ገን
ዘባቸውንም ፡ እንዳይወስዱባቸው ፡ የንጉሡ ፡
ደብዳቤ ፡ ታዘዘ ።
ንስሐ ፡ ገብተው ፡ በጮሁ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፳፰
እንዲህ ፡ አድርጎ ፡ እስራኤልን ፡ ይቅር ፡ ይላቸ
ዋልና ፡ በኖሩበት ፡ በፋርስ ፡ አገር ፡ ይወዷቸው ፡
ያከብሩዋቸው ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ አገራቸ
ውን ፡ እንዳያጠፉ ፡ ከብቶቻቸውንም ፡ እንዳይ
ዘርፉ ፡ የንጉሥ ፡ ደብዳቤ ፡ ታዘዘ ።
ባሳዘኑትም ፡ ጊዜ ፡ የሚያስጨንቋቸው ፡ አሕ ፳፱
ዛብን ፡ ያስነሣባቸዋል ፡ ረዳታቸውን ፡ ይሰድላ
ቸው ፡ ዘንድ ፡ መከራ ፡ ከሚያጸኑባቸው ፡ ከአ
ሕዛብም ፡ እጅ ፡ ያድናቸው ፡ ዘንድ ፡ የዚያን ፡
ጊዜ ፡ ፈጽመው ፡ ያለቅሳሉ ፡ ይጮኻሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፱ ።

የግብጽም ፡ ሰዎች ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ፩
በጭንቅ ፡ ጡብ ፡ በማሠራት ፡ ባሠሯቸውም ፡
ጊዜ ፡ ሥራውን ፡ ሁሉ ፡ ያለገለባም ፡ ጭቃ ፡
በመርገጥ ፡ ጡብንም ፡ በመትከስ ፡ ባስጨነቋ
ቸው ፡ ጊዜ ።
ሠሪዎችን ፡ የሚያፋጥኑ ፡ አለቆችንም ፡ በነርሳ ፪
ቸው ፡ ሾመው ፡ ባሠሯቸውም ፡ ጊዜ ፡ የግብጽን ፡
ጡብ ፡ ሁሉ ፡ ከመሥራት ፡ ያድናቸው ፡ ዘንድ ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮሁ ።
የዚያን ፡ ጊዜ ፡ የሚረዷቸው ፡ አሮንና ፡ ሙሴን ፡ ፫
ሰደደላቸው ፡ ከፈርዖን ፡ አገዛዝ ፡ ቤት ፡ ወገኖ
ቹን ፡ ያወጡ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ልኳቸዋ
ልና ፡ ከጡብም ፡ ሥራ ፡ አዳኗቸው ፡ እንዳይገዙ ፡
ለእግዚአብሔርም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ መሥዋ
ዕት ፡ እንዳይሠዉ ፡ በትዕቢቱ ፡ እስራኤልን ፡

ማስናበት ፡ እምቢ ፡ ስላሉ ፡ ወገኖቹን ፡ እስራኤ
ልን ፡ ከግብጽ ፡ ንጉሥ ፡ ከፈርዖን ፡ እገዛዝ ፡ ቤት ፡
ያወጧቸው ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ልኳቸዋ
ልና ፡ አዳኗቸው ።
፬፤ እግዚአብሔር ፡ ትዕቢተኞችን ፡ ቸል ፡ ይላቸዋ
ልና ፡ ፈርዖንንም ፡ ስለ ፡ ትዕቢቱ ፡ ከሠራዊቱ ፡
ጋራ ፡ በኤርትራ ፡ ባሕር ፡ አሰጠመው ።
፭፤ መኳንንትና ፡ ነገሥታት ፡ ሲሆኑ ፡ የእግዚአብ
ሔርን ፡ ቃል ፡ ቸል ፡ የሚሉ ፡ ፈቃዱንም ፡ ይፈ
ጽሙለት ፡ ዘንድ ፡ በበጎም ፡ ነገር ፡ ለሚያገለ
ግሉ ፡ ሰዎች ፡ ደሞዛቸውን ፡ ይሰጧቸው ፡ ዘንድ ፡
ገናና ፡ ስሙንም ፡ ያከብሩ ፡ ዘንድ ፡ በሾማቸው ፡
በነገሣቸው ፡ መንግሥት ፡ ሁሉ ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡
ያልሠሩትን ፡ እንደሱ ፡ ያጠፋቸዋል ።
፮፤ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ እግዚአብሔር ፡ መንግሥቱን ፡
ቢያቀኑ ፡ ግን ፡ መንግሥታቸውን ፡ አቀናላቸዋ
ለሁ ፡ አለ ።
፯፤ በጎ ፡ ሥራ ፡ ሥሩልኝ ፡ እኔም ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ እሠ
ራላችኋለሁ ፡ ሕጌን ፡ ጠብቁ ፡ እኔም ፡ ሰውነታ
ችሁን ፡ እጠብቃችኋለሁ ፡ በሕጌ ፡ ጸንታችሁ ፡
ኑሩ ፡ እኔም ፡ እንደ ፡ ልቡናችሁ ፡ ቅንነትን ፡
አሳድሬባችሁ ፡ እኖራለሁ ።
፰፤ እኔን ፡ ውደዱ ፡ እኔም ፡ ደኅንነታችሁን ፡ እወዳ
ለሁ ፡ ወደኔ ፡ ተጠጉ ፡ እኔም ፡ አድናችኋለሁ ።
፱፤ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ እግዚአብሔር ፡ በኔ ፡ እመኑ ፡
እኔም ፡ ከመከራው ፡ አድናችኋለሁ ፡ አለ ።
፲፤ ባጠገብ ፡ ባጠገብ ፡ አትኑሩ ፡ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡
እግዚአብሔር ፡ የቀና ፡ ሥራን ፡ ይወዳልና ፡
እናንተ ፡ ወደኔ ፡ ቅረቡ ፡ እኔም ፡ ወደናንተ ፡
እቀርባለሁ ፡ አለ ፡ ኃጢአተኞች ፡ ከዳተኞች ፡
የምትሆኑ ፡ ሰዎች ፡ እጃችሁን ፡ ከኃጢአት ፡
አንጹ ፡ ልቡናችሁንም ፡ ከክፋት ፡ አርቁ ።
፲፩፤ እኔም ፡ ቍጣየን ፡ ከናንተ ፡ አርቃለሁ ፡ በቸርነ
ትና ፡ በይቅርታም ፡ እመለስላችኋለሁ ።
፲፪፤ በደልን ፡ የሚሠሩ ፡ ወንጀለኞች ፡ ጠላቶች
ንም ፡ ከናንተ ፡ አርቃለሁ ፡ በረያዩ ፡ ዳዊትን ፡
ከተገናኙት ፡ ከጠላቶቹ ፡ ከብዙ ፡ ተንከላቸው ፡
አርበኛ ፡ ከሆነ ፡ ከጐልያድም ፡ እጅ ፡ ይገድ
ለውም ፡ ዘንድ ፡ ከፈለገው ፡ ከሳኦልም ፡ እጅ ፡
መንግሥቱን ፡ ይወስድ ፡ ዘንድ ፡ ከወደደ ፡
ከልጁ ፡ ከአቤሴሎምም ፡ እጅ ፡ እንዳዳንኩት ።
፲፫፤ ሕጌን ፡ የሚጠብቁ ፡ ፈቃዴንም ፡ የሚፈጽሙ ፡
ሰዎችን ፡ እንደሱ ፡ አድናቸዋለሁ ፡ ክብርን ፡
አወርሳቸዋለሁ ፡ በወዲህም ፡ ዓለም ፡ በሚመጣ
ውም ፡ ዓለም ፡ በወዲያኛው ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፡
ደስ ፡ ይላቸው ፡ ዘንድ ፡ በሁሉ ፡ ላይ ፡ አነግሣቸ
ዋለሁ ።
፲፬፤ እርሱ ፡ ሕፃን ፡ ሆኖ ፡ ሳለ ፡ ከሕፃንነቱ ፡ ጀምሮ ፡
ባማረ ፡ አኗኗሩ ፡ እግዚአብሔር ፡ የመረጠው ፡
ነቢዩ ፡ ሳሙኤል ፡ እንዳገለገለው ፡ ባማረ ፡ አኗ
ኗራቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ካገለገሉ ፡ ከከበሩ ፡
ነገሥታት ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ይሆናሉ ።
፲፭፤ አገልጋይ ፡ ሽማግሌ ፡ ለሆነ ፡ ለኤሊ ፡ ይነግረው ፡
ዘንድ ፡ ነገረው ፡ በእግዚአብሔርም ፡ ማደሪያ ፡
በቤተ ፡ መቅደስ ፡ ሲያገለግል ፡ የሳሙኤልም ፡
ሥራው ፡ የማረ ፡ የተወደደ ፡ ነበር ።
በእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ በቤተ ፡ መቅደስም ፡ ፲፮፤
ሲያገለግል ፡ በደገ ፡ ጊዜ ፡ ሕዝቡን ፡ ይሾም ፡
ዘንድ ፡ ነገሥታቱንም ፡ በእግዚአሔር ፡ ፈቃድ ፡
ይቀባ ፡ ዘንድ ፡ እንዲሾም ፡ እንዲቀባ ፡ አደረ
ገው ። እግዚአብሔር ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡
የመረጠው ፡ ወገን ፡ ይሾም ፡ ዘንድ ፡ ወዶታልና ፡
የፈጠረው ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ፈቃድ ፡ በፈ
ጸመ ፡ ጊዜ ፡ በእጁ ፡ ቅብዓ ፡ መንግሥትን ፡
ሰጠው ።
ሳኦልም ፡ በመንግሥቱ ፡ ሳለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፲፯፤
ነቢዩ ፡ ሳሙኤልን ፡ ሂደህ ፡ ከይሁዳ ፡ ወገን ፡
የተወለደ ፡ የሶሚይ ፡ ልጅ ፡ ዳዊትን ፡ ወድጄዋ
ለሁና ፡ ቅባው ፡ አለው ።

## ምዕራፍ ፡ ፴ ።

ቃሌን ፡ ስለ ፡ ተደፋፈረ ፡ አሳዝኖኛልና ፡ የሳ ፩፤
ኦልን ፡ ወገን ፡ ጠላሁ ።
እኔም ፡ ቸል ፡ አልኩት ፡ ሕጌን ፡ አልጠበቀምና ፡ ፪፤
ዳግመኛም ፡ ከወገኑ ፡ አላነግሥም ።
ሕጌንና ፡ ቃሌን ፡ ሥርዓቴንም ፡ ያልጠበቁ ፡ ሰዎ ፫፤
ችም ፡ እንደሱ ፡ መንግሥቴንና ፡ ስጦታዬን ፡
እስከ ፡ ዘለዓለሙ ፡ ድረስ ፡ ከልጆቻቸው ፡ አጠ
ፋለሁ ።
በገነንኳቸውም ፡ ጊዜ ፡ አላገነኑኝምና ፡ አጠፋ ፬፤
ቸዋለሁ ፡ እንጂ ፡ ዳግመኛ ፡ እንዳነግሣቸው ፡ አል
መለስም ፡ ባከብራቸውም ፡ አላከበሩኝምና ፡
አላገናቸውም ።
በጎ ፡ ነገርን ፡ ባደረግሁላቸው ፡ ጊዜ ፡ በጎ ፡ ነገ ፭፤
ርን ፡ አያደርጉልኝምና ፡ ይቅርም ፡ ባልኋቸው ፡
ጊዜ ፡ ይቅር ፡ አላሉኝምና ።
በሁሉም ፡ ላይ ፡ ገዥ ፡ ባደረግኋቸው ፡ ጊዜ ፡ ፮፤
ገዥ ፡ አላደረጉኝምና ፡ ከሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ባከበ
ርኋቸው ፡ ጊዜ ፡ አላከበሩኝምና ፡ ዳግመኛ ፡ አላ
ገናቸውም ፡ አላከብራቸውም ፡ ሕጌንም ፡ አል
ጠበቁምና ።
እኔም ፡ የሰጠኋቸውን ፡ ስጦታ ፡ ነሳኋቸው ፡ ተቈ ፯፤
ጥቼም ፡ እንደ ፡ ማልሁ ፡ መጠን ፡ የነሳኋቸውን ፡
ገንዘብ ፡ አልመልስላቸውም ፡ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡
እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡ ያከበሩኝን ፡ አከ
ብራቸዋለሁ ፡ የወደዱኝንም ፡ እወዳቸዋለሁ ፡
አለ ።
ያላከበሩኝ ፡ ሕጌንም ፡ ያልጠበቁትን ፡ ከሰጠኋ ፰፤
ቸው ፡ ስጦታ ፡ እለያቸዋለሁ ።
ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ እግዚአብሔር ፡ አለ ፡ የወደደ ፱፤
ኝን ፡ እወደዋለሁ ፡ ያገነነኝን ፡ አገነዋለሁ ፡ አለ ።
እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሁሉን ፡ የምገዛ ፡ ነኝና ፡ ፲፤
በምድርና ፡ በሰማይ ፡ ከሥልጣኔ ፡ የሚያመልጥ ፡
የለም ፡ የምገድል ፡ የማድን ፡ የማሳዝንና ፡ ይቅር ፡
የምል ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝና ።
ገናንነት ፡ ክብርም ፡ የኔ ፡ ገንዘብ ፡ ነውና ፡ የወ ፲፩፤
ደድሁትን ፡ አከብረዋለሁ ፡ የምፈርድ ፡ ተበቃዩ ፡
የማጠፋ ፡ እኔ ፡ ነኝና ፡ የጠላሁትንም ፡ አጐ

ሰቀሉዋለሁ ።
፲፪፤ የሚወዱኝ ፡ ስሚንም ፡ ሁለጊዜ ፡ የሚጠሩትን ፡
ይቅር ፡ የምል ፡ እኔ ፡ ነኝና ፡ ለበለጠጋውና ፡
ለድኃው ፡ ምግብ ፡ የምመግብ ፡ እኔ ፡ ነኝና ።
፲፫፤ ወፎችንና ፡ እንስሶችንም ፡ በበሕር ፡ ያሉ ፡ ዓሣ
ዎችንና ፡ አውሬዎችን ፡ እባቦችንም ፡ እመግብ
ለሁ ፡ እንጂ ፡ ሰውን ፡ ብቻ ፡ የምመግብ ፡ አይደ
ለሁም ።
፲፬፤ አዞዎችንና ፡ ዓሣንበሪዎችን ፡ አሽኮኮዎችና ፡
ጉማሬዎችን ፡ አቀስጣንም ።
፲፭፤ በውኃ ፡ ውስጥም ፡ የሚኖረውን ፡ ሁሉ ፡ በነፋስ ፡
ላይ ፡ የሚበረውን ፡ ሁሉ ፡ እመግበለሁ ፡ እንጂ ፡
ሰውን ፡ ብቻ ፡ የምመግብ ፡ አይደለሁም ፡ ይህ ፡
ሁሉ ፡ የኔ ፡ ገንዘብ ፡ ነው ።
፲፮፤ በሚገባ ፡ በሚወደድም ፡ ሁሉ ፡ እኔን ፡ የሚፈ
ልጉኝን ፡ ሁሉ ፡ የምመግብ ፡ እኔ ፡ ነኝ ።

ምዕራፍ ፡ ፴፩ ።

፩፤ ነገሥታቱም ፡ ያለኔ ፡ ፈቃድ ፡ አይነግሡም ፡
ጦም ፡ አዳሪዎችም ፡ በትእዛዜ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡
ያለ ፡ ትእዛዜ ፡ አይደኸዩም ፡ ኃይለኞችም ፡ በፈ
ቃዴ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ያለ ፡ ፈቃዴ ፡ አይበረቱም ።
፪፤ እኔ ፡ ለዳዊት ፡ መወደድን ፡ ለሰሎሞን ፡ ጥበብን ፡
ሰጠሁት ፡ ለሕዝቅያስም ፡ ዘመኖችን ፡ ጨመር
ሁለት ።
፫፤ የጎልያድን ፡ ዘመን ፡ አሳንስሁ ፡ እኔ ፡ ለሶምሶ
ንም ፡ ኃይልን ፡ ሰጠሁት ፡ ዳግመኛም ፡ ኃይሉን ፡
አደከምሁ ።
፬፤ በሪያዬ ፡ ዳዊትንም ፡ እኔ ፡ አርበኛ ፡ ከሆነ ፡ ከጎ
ልያድ ፡ እጅ ፡ አዳንኩት ።
፭፤ ዳግመኛም ፡ ከንጉሡ ፡ ከሳኦል ፡ እጅ ፡ ከተከራ
ከረውም ፡ ከሁለተኛው ፡ አርበኛ ፡ አዳንሁት ፡
ትእዛዜንም ፡ ጠብቋልና ፡ ከሚከራከሩትም ፡
ከሚጠሉትም ፡ ሰዎች ፡ እጅ ፡ አዳንሁት ።
፮፤ እኔም ፡ እሱን ፡ ወደድሁ ፡ ሕጌን ፡ የሚጠብቁ ፡
መኳንንቱና ፡ ነገሥታቱም ፡ ሁሉ ፡ እወዳቸዋ
ለሁ ፡ እነሳቸው ፡ ደስ ፡ አሰኝተውኛልና ፡ በጠ
ላቶቻቸው ፡ ላይ ፡ ድል ፡ መንሣትንና ፡ ኃይልን ፡
እሰጣቸዋለሁ ።
፯፤ ዳግመኛም ፡ ያባቶቻቸውን ፡ ምድር ፡ ይወርሱ ፡
ዘንድ ፡ ላባቶቻቸው ፡ የማልኩላቸውን ፡ የነ
ጻች ፡ የበራች ፡ ምድረ ፡ ርስትን ፡ እሰጣቸዋለሁ ።

ምዕራፍ ፡ ፴፪ ።

፩፤ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ እግዚአብሔር ፡ እናንተም ፡
መኳንንቱና ፡ ነገሥታቱም ፡ ቃሌን ፡ ስሙኝ ፡
ትእዛዜንም ፡ ጠብቁ ፡ አለ ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡
ፈጣሪያቸው ፡ ስሆን ፡ የጠበቅኋቸው ፡ ያዳንኋ
ቸው ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዳሳዘኑኝ ፡ ልዩ ፡
የሆኑ ፡ ጣዖቶችንም ፡ እንዳመለኩ ፡ እንዳታሳዝ
ኑኝ ፡ እንዳታመልኩ ፡ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ቃሌን ፡ ስሙኝ ፡ አለ ፤ ከባት ፡ ከናታ
ቸውም ፡ ከተወለዱ ፡ ጀምሮ ፡ ያሳደግኋቸው ፡
የወደዱትንም ፡ ሁሉ ፡ የመገብኋቸው ።
ወደ ፡ ምድርም ፡ አዝመራ ፡ ያወጣኋቸው ፡ እን ፪፤
ደሚገባም ፡ አድርጌ ፡ ከምድር ፡ የተገኘውን ፡
ድልብ ፡ የመገብኋቸው ፡ ያልተከሉትንም ፡ የወ
ይኑን ፡ ሐረግ ፡ የዘይቱንም ፡ ፍሬ ፡ ያልቆፈሩ
ትን ፡ የጠራ ፡ የውኃውንም ፡ ጉድጓድ ፡ የሰጠ
ኋቸው ።
ፈጣሪያቸው ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ስሆን ፡ ጣዖ ፫፤
ቶችን ፡ አምልከው ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እን
ዳሳዘኑኝ ፡ እንዳታሳዝኑኝ ፡ ቃሌን ፡ ስሙኝ ፡ እላ
ቸው ፡ ከተፈቱገው ፡ ስንዴ ፡ ጋራ ፡ የበጉን ፡ ወተ
ትና ፡ የማሩን ፡ ወለላ ፡ የመገብኋቸው ፡ ጌጥ ፡ ያለ
በት ፡ ልብስንም ፡ ያለበስኋቸው ፡ የሚወደደው
ንም ፡ ሁሉ ፡ የሰጠኋቸው ።
የለመኑኝንም ፡ ሁሉ ፡ ያሳጣኋቸው ፡ ሳይኖር ። ፬፤

ምዕራፍ ፡ ፴፫ ።

ዳዊት ፡ መላእክት ፡ ያወረዱትን ፡ መና ፡ የእ ፩፤
ስራኤል ፡ ልጆች ፡ ተመገቡ ፡ ብሎ ፡ እንደ ፡ ተና
ገረ ፡ ዳግመኛም ፡ የሚጣፍጥ ፡ መናን ፡ በምድረ ፡
በዳ ፡ የመገብኋቸው ፡ እኔ ፡ ፈጣሪያቸው ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ስሆን ፡ ጣዖታቱን ፡ አምልከው ፡
የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንዳሳዘኑኝ ፡ እንዳታሳ
ዝኑኝ ፡ ቃሌን ፡ ስሙኝ ፡ አለ ፡ በሚገባና ፡ በው
ነት ፡ ያመልኩኝ ፡ ዘንድ ፡ ይኸንን ፡ ሁሉ ፡ አደ
ረግሁላቸው ።
ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ እግዚአብሔር ፡ እነሳቸው ፡ ፪፤
ግን ፡ አላመለኩኝም ፡ እኔም ፡ ቻል ፡ አልኋቸው ፡
አለ ፡ አሳዘኑኝ ፡ የኔ ፡ ሕግ ፡ ባልሆነ ፡ በሕገ ፡ ጣዖ
ትም ፡ ጸንተው ፡ ኖሩ ።
እኔም ፡ እንደ ፡ ኃጢአታቸው ፡ ፍዳውን ፡ አመ ፫፤
ጣባቸዋለሁ ፡ አምልኮቴን ፡ ቻል ፡ ብለዋልና ፡
በምክሬና ፡ በሥርዓቴም ፡ አልጸኑምና ፡ በእጃ
ቸው ፡ እንደ ፡ ሠሩት ፡ ኃጢአት ፡ መጠን ፡ ቻል ፡
አልኋቸው ፡ በሰማይ ፡ በሚደረግ ፡ ቍርጥ ፡
ፍርድ ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡ አወርዳቸዋለሁ ።
ሕጌን ፡ አልጠበቁምና ፡ እኔም ፡ እቈጣቸዋለሁና ፡ ፬፤
በዚህ ፡ ዓለምም ፡ ዘመናቸውን ፡ አሳንሳለሁ ።
አንተ ፡ ንጉሥን ፡ ብትሆን ፡ የምትሞት ፡ የምት ፭፤
ፈርስ ፡ ነገ ፡ ትል ፡ ትቢያ ፡ የምትሆን ፡ ሰው ፡
አይደለህምን ።
ዛሬ ፡ ግን ፡ ለዘለዓለሙ ፡ እንደማይሞት ፡ ሰው ፡ ፮፤
ትመካለህ ፡ ትኩራለህ ።
ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዛሬ ፡ ደኅና ፡ ፯፤
ሁነህ ፡ የምትታይ ፡ አንተ ፡ ግን ፡ ነገ ፡ የምት
ሞት ፡ ሰው ፡ ነህ ፡ አለ ።
ትእዛዜንና ፡ ቃሌን ፡ ብትጠብቁ ፡ ግን ፡ ማደሪያ ፰፤
ቸው ፡ ብርሃን ፡ ከሆነ ፡ ዘውዶቻቸውም ፡ ከማሩ ፡
ዙፋኖቻቸውም ፡ የብርና ፡ የወርቅ ፡ ከሆኑ ፡ በነ
ሳቸውም ፡ ላይ ፡ የሚቀመጡ ፡ ሰዎች ፡ ያጌጡ ፡
ከሆኑ ፡ ፈቃዴን ፡ ከደረጉ ፡ ከከበሩ ፡ ነገሥታት ፡
ጋራ ፡ የከበረች ፡ አገርን ፡ አወርስሀለሁ ፡ አለ ።
በጎ ፡ ሥራን ፡ ለሠሩ ፡ ሰዎች ፡ የቀረበች ፡ በታ ፡ ፱
በምትሆን ፡ በገነም ፡ ውስጥ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
ሥርዓቴንና ፡ ሕጌን ፡ አልጠበቁምና ፡ ኃጢአት ፡ ፲፤

ለሚሠሩ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ የከበሩ ፡ ነገሥታት ፡ ወደሚገቡ
በት ።
፲፩፤ ወደዚያች ፡ አገር ፡ ይገቡ ፡ ዘንድ ፡ አይገቡቸ
ውም ፡ አለ ።

ምዕራፍ ፡ ፴፬ ።

፩፤ የሚዶን ፡ መንግሥት ፡ ትጠፋለች ፡ የሮም ፡
መንግሥት ፡ ግን ፡ በመቄዶንያ ፡ መንግሥት ፡
ላይ ፡ ፈጽማ ፡ ትጸናለች ፡ የነነዌም ፡ መንግሥት ፡
በፋርስ ፡ መንግሥት ፡ ላይ ፡ ትጸናለች ።
፪፤ የኢትዮጵያ ፡ መንግሥትም ፡ በእስክንድርያ ፡
መንግሥት ፡ ላይ ፡ ትጸናለች ፡ አሕዛብ ፡ ይነሣ
ሉና ፡ የሞዓብ ፡ መንግሥት ፡ በአማሌቅ ፡ መን
ግሥት ፡ ላይ ፡ ትጸናለች ።
፫፤ ወንድም ፡ በወንድሙ ፡ ላይ ፡ ይነሣል ፡ ይጠፋ ፡
ዘንድ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ተበ
ቅሎ ፡ ያጠፋል ።
፬፤ መንግሥት ፡ በመንግሥት ፡ ላይ ፡ ሕዝቡም ፡
በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ አገርም ፡ በአገር ፡ ላይ ፡ ይነ
ሣል ፡ አለ ።
፭፤ ክርክርም ፡ ይደረጋል ፡ ሰልፍ ፡ ረኃብ ፡ ቸነፈር ፡
ንውጥውጥታ ፡ ድርቅ ፡ ይሆናል ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡
ፍቅር ፡ ጠፍቷልና ፡ የእግዚአብሔር ፡ መቅሠ
ፍት ፡ በርሷ ፡ ወረደ ።
፮፤ ከምሥራቅ ፡ እስከ ፡ ምዕራብ ፡ እንደሚታይ ፡
መብረቅ ፡ የምታስፈራ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚ
መጣበት ፡ ቀን ፡ ድንገት ፡ ደርሳለችና ።
፯፤ እሱ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፍርድ ፡ በሚፈርድበት ፡
ቀን ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ እጁ ፡
ድካምና ፡ እንደ ፡ ኃጢአቱም ፡ ጽናት ፡ ፍዳውን ፡
ይቀበላል ፡ እሱ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፍርድ ፡ በሚ
ፈርድበት ፡ ቀን ፡ እግራቸውም ፡ በሚሰነካከል
በት ፡ ቀን ፡ እበቀላቸዋለሁ ፡ ብሏልና ፡ ለጥፋት ፡
የሚቈጠሩበት ፡ ቀን ፡ ደርሷልና ።
፰፤ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሕጉ ፡ ጸን
ተው ፡ የማይኖሩ ፡ ኃጢአት ፡ የሚሠሩ ፡ ሰዎ
ችን ፡ ለዘለዓለሙ ፡ በገሃነም ፡ ያጠፋቸዋል ፡
የቆጵሮስና ፡ የይሁዳ ፡ የደማስቆና ፡ የሰማርያም ፡
ሰዎች ፡ የባቢሎን ፡ ሰዎች ።
፱፤ በምዕራብ ፡ ደሴትም ፡ የሚኖሩ ፡ የኖባና ፡ የሕ
ንደኬም ፡ የሳባ ፡ የኢትዮጵያና ፡ የግብጽም ፡
ሰዎች ፡ በነሳቸው ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ።
፲፤ ምድርና ፡ ሰማይን ፡ እምገዛ ፡ መወደድንና ፡ ክብ
ርንም ፡ እምሰጥ ፡ እማድንና ፡ እምገድልም ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ እኔ ፡ እንደ ፡ ሆንኩ ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡
ያውቁኛል ።
፲፩፤ ፀሐይን ፡ የማወጣ ፡ ወደ ፡ መግቢያው ፡ እምል
ከው ፡ ክፉውንና ፡ በጎውንም ፡ እማመጣ ፡ እኔ ፡
ነኝ ።
፲፪፤ እማታውቋቸውን ፡ የደከማችሁበትን ፡ ገንዘብ ፡
የበጎቻችሁንና ፡ የላሞቻችሁንም ፡ መንጋ ፡ አር
ደው ፡ የሚበሉ ፡ አሕዛብን ፡ እማመጣ ፡ እኔ ፡ ነኝ ።
፲፫፤ ልጆቻችሁንም ፡ በፊታችሁ ፡ እየቀጠቀጡ ፡
ይማርኳቸዋል ፡ እለሳቸውንም ፡ ማዳን ፡ አትች
ሉም ። የእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ ረድኤት ፡
ስላላደረበችሁ ፡ የሰማችሁትን ፡ የእግዚአብሔ
ርን ፡ ትእዛዝ ፡ አልፈራችሁምና ፡ ቅምጥላች
ሁን ፡ ድልድላችሁን ፡ ያጠፋሉ ።
በንት ፡ ያደረ ፡ የእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ ረድ ፲፬፤
ኤትን ፡ አያለሁና ፡ ብሎ ፡ ናቡከደነፆር ፡ ለዳን
ኤል ፡ እንደ ፡ ነገረው ፡ የእግዚአብሔር ፡ መን
ፈስ ፡ ረድኤት ፡ ያደረበት ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ሁሉን ፡
ያውቃል ።
የእግዚአብሔርም ፡ መንፈስ ፡ ረድኤት ፡ ያደረ ፲፭፤
በት ፡ ሰው ፡ ሁሉን ፡ ያውቃል ፡ የተሠወረውም ፡
ይገለጥለታል ፡ የተገለጠውንና ፡ የተሠወረው
ንም ፡ ሁሉ ፡ ያውቃል ፡ እንጂ ፡ የእግዚአብሔር ፡
መንፈስ ፡ ረድኤት ፡ ካደረበት ፡ ሰው ፡ የሚሠ
ወር ፡ የለም ።
እኛ ፡ ግን ፡ ነገ ፡ የምንሞት ፡ ሰዎች ፡ ነንና ፡ ሠወ ፲፮፤
ረን ፡ የሠራነው ፡ ኃጢአታችን ፡ ይገለጣል ።
ብርንና ፡ ወርቅንም ፡ በእሳት ፡ እንዲፈትኑት ፡ ፲፯፤
የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ አልጠበቁምና ፡
ኃጥአን ፡ እንዲሉ ፡ ኋላ ፡ በዕለተ ፡ ምጽአት ፡
ይመረመራሉ ።
የዚያን ፡ ጊዜ ፡ የአሕዛብ ፡ ሁሉና ፡ የእስራኤል ፡ ፲፰፤
ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ሥራዎቻቸው ፡ ይመረመራሉ ።

ምዕራፍ ፡ ፴፭ ።

አባት ፡ እናቱ ፡ ለሞቱበት ፡ ልጅ ፡ እውነት ፡ ፩፤
ፍርድ ፡ ስላልፈረዳችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ በናንተ ፡
ላይ ፡ ይቈጣልና ፡ የእስራኤል ፡ መኳንንቶች ፡
ወዮላችሁ ።
ጢትና ፡ ማታ ፡ ወደ ፡ መሸተኛ ፡ ቤት ፡ የምት ፪፤
ሔዱ ፡ የምትሰክሩ ፡ ፍርድ ፡ የምታደሉ ፡ የበ
ልቴቱና ፡ እናት ፡ አባቱ ፡ የሞቱበት ፡ ልጅ ፡
ፍርድንም ፡ የማትሰሙ ፡ በኃጢአትና ፡ በመዳ
ራትም ፡ የምትኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ወዮላችሁ ።
እግዚአብሔር ፡ የእስራኤል ፡ መኳንንቶችን ፡ ፫፤
እንዲህ ፡ አላቸው ፡ በትእዛዜ ፡ ጸንታችሁ ፡ ካል
ኖራችሁ ፡ ሕጌንም ፡ ካልጠበቃችሁ ፡ እኔ ፡ የም
ወደውን ፡ ካልወደዳችሁ ፡ ወዮላችሁ ፡ አላ
ቸው ።
እኔም ፡ ጥፋትንና ፡ መቅሠፍትን ፡ መከራን ፡ ፬፤
አመጣባችኋለሁ ፡ ነቀዝና ፡ ብልም ፡ እንደበ
ላው ፡ ትጠፋላችሁ ፡ ፍለጋችሁና ፡ አውራጃች
ሁም ፡ አይገኝም ፡ አላቸው ።
አገራችሁም ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ትሆናለች ፡ ቀድ ፭፤
ሞም ፡ ያያት ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ እጁን ፡ ያጨበጭ
ባል ፡ ይች ፡ አገር ፡ በረከቷን ፡ የሚወደውንም ፡
ሁሉ ፡ የተመላች ፡ አልነበረችምን ፤ እግዚአብ
ሔር ፡ በሚኖሩባት ፡ ሰዎች ፡ ኃጢአት ፡ እንዲህ ፡
አደረጋት ፡ እያለ ፡ በርሷ ፡ ይደነቃል ።
ልዑን ፡ አሆርታለችና ፡ ራሷንም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ፮፤
አድርጋለችና ፡ እግዚአብሔር ፡ በመሬት ፡ እስ
ኪያገሳቅላት ፡ ድረስ ፡ ከዛደ ፡ ልቡናዋንም ፡
አጽንታለችና ፡ በሚኖሩባት ፡ ሰዎች ፡ ትዕቢ

ትም ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ትሆናለችና ፡ ከአሚከላ ፡ ጋራ ፡ እሾህም ፡ በቅሎባታልና ፡ ወዮላት ፡ ይላሉ ።
፯፤ ሙጃንና ፡ እስተናግርም ፡ አበቀለች ፡ ምድረ ፡ በዳና ፡ በረሃንም ፡ ሆነች ፡ አውሬዎችም ፡ በውስጧ ፡ ይኖሩባታል ።
፰፤ የእግዚአብሔር ፡ ፍርድ ፡ በርሷ ፡ ጸንቷልና ፡ በሚኖሩባትም፡ሰዎች፡ኃጢአት፡ስለ፡ልቡናዋ፡ ትዕቢት ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ፍርድ ፡ ጽዋ ፡ ተቀብላለችና ፡ ወደርሷ ፡ ለሚሔዱ ፡ ሰዎችም ፡ የምታስፈራ ፡ ሆነች ።

ምዕራፍ ፡ ፴፬ ።

፩፤ የመቄዶን ፡ ሰዎች ፡ አትመኩ ፡ ተበቅሎ ፡ የሚያጠፋችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ አለና ፡ አማሌቃውያን ፡ ክፉደ ፡ ልቡናችሁን ፡ አታጽኑ ።
፪፤ እስከ ፡ ሰማይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ትላላችሁና ፡ እስከ ፡ ገሃነምም ፡ ትወርዳላችሁና ።
፫፤ እስራኤል ፡ ቀድሞ ፡ በሞዓብና ፡ በሚዶን ፡ መንግሥት ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ አገር ፡ በገቡ ፡ ጊዜ ፡ ትገዳደሩት ፡ ዘንድ ፡ በእግዚአብሔር ፡ መገዳደር ፡ አይገባምና ፡ አትመኩ ፡ አለ ።
፬፤ አንተ ፡ የይስማኤል ፡ ወገን ፡ የብርያ ፡ ልጅ ፡ ያንተ ፡ ገንዘብ ፡ ባልሆነ ፡ ክፉደ ፡ ልቡናህን ፡ ለምን ፡ ታጸናለህ ፡ በምድርስ ፡ ይፈረድበት ፡ ዘንድ ፡ በተነሣ ፡ ጊዜ ፡ በሚፈረድብህ ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲፈርድብህ ፡ አታስብምን ።
፭፤ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ እግዚአብሔር ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ እንደጅህ ፡ ሥራ ፡ ፍዳህን ፡ ትቀበላለህ ፡ ልቡናህንስ ፡ ለምን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ታደርጋለህ ፡ ክፉደ ፡ ልቡናህንስ ፡ ለምን ፡ ታጸናለህ ፡ አለ ።
፮፤ ወገኖችህ ፡ ባልሆኑ ፡ ሰዎች ፡ አንተ ፡ እንደተገዳደርህ ፡ እኔም ፡ እገዳደርሃለሁ ፡ ኃጢአትን ፡ ትሠራ ፡ ዘንድ ፡ የወደድኸውን ፡ ታደርጋለህና ፡ በላኩህም ፡ በታ ፡ ቶል ፡ እልሃለሁ ።
፯፤ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ እግዚአብሔር ፡ እኔም ፡ ባንተ ፡ ላይ ፡ እንዲህ ፡ አደርጋለሁ ፡ አለ ፡ አንተ ፡ ግን ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ ከሠራህ ፡ እኔ ፡ እምወደውን ፡ ከወደድህ ፡ እኔም ፡ የለመንከውን ፡ ሁሉ ፡ እሰማሃለሁ ፡ አለ ።
፰፤ የእኔን ፡ ፈቃድ ፡ ብትፈጽምልኝ ፡ ያንተንም ፡ ፈቃድ ፡ እፈጽምልሃለሁ ፡ ጠላቶችህንም ፡ እክራከርልሃለሁ ፡ ልጆችህንና ፡ ዘርህንም ፡ እባርክልሃለሁ ።
፱፤ የበጎችህንና ፡ የላሞችህንም ፡ መንጋ ፡ አበዛልሃለሁ ፡ በትእዛዜ ፡ ጸንተህ ፡ ከኖርህ ፡ እኔም ፡ የምወደውንም ፡ ከደረግህ ፡ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእጅህ ፡ የያዝከውን ፡ ሁሉ ፡ እባርክልሃለሁ ፡ አለ ።
፲፤ ፈቃዴን ፡ ባታደርግ ፡ በሕጌና ፡ በትእዛዜ ፡ ጸንተህ ፡ ባትኖር ፡ ግን ፡ ቀድሞ ፡ የተነገረው ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ መከራ ፡ ያገኝሃል ፡ በትእዛዜ ፡ ጸንተህ ፡ መከራን ፡ አልታገሥህምና ፡ በሕጌም ፡ ጸንተህ ፡ አልኖርክምና ፡ ሁለጊዜ ፡ ከምትመጣብህ ፡ ቍጣዬም ፡ ማምለጥ ፡ አትችልም ።
፲፩፤ እኔ ፡ የወደድሁትንም ፡ አልወደድህምና ፡ እኔ ፡ ከለመኖር ፡ ወደ ፡ መኖር ፡ አምጥቼ ፡ የፈጠርሁህ ፡ ሲሆን ።
፲፪፤ የወደድኸውን ፡ ሁሉ ፡ ልታደርግ ፡ ትገድል ፡ ታድን ፡ ዘንድ ፡ ትሠራ ፡ ታፈርስ ፡ ዘንድ ፡ ታከብር ፡ ታጐሰቍል ፡ ዘንድ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ታደርግ ፡ ታዋርድም ፡ ዘንድ ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ ያንተ ፡ ገንዘብ ፡ ነበር ፡ በሥልጣንህ ፡ በታች ፡ ባሉ ፡ ሰዎች ፡ ዘንድም ፡ ጌትነትንና ፡ ክብርንም ፡ የሰጠሁህ ፡ እኔ ፡ ስሆን ፡ አምልኮቴንና ፡ ምስጋናዬንም ፡ ቶል ፡ ብለሃልና ፡ ከምትመጣብህ ፡ ቍጣዬ ፡ ማምለጥ ፡ አትችልም ።
፲፫፤ የእግዚአብሔርንም ፡ ፈቃድ ፡ ከደረግህ ፡ በትእዛዙም ፡ ጸንተህ ፡ ከኖርህ ፡ በጌትነቱ ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ ደስ ፡ ይልህ ፡ ዘንድ ፡ የከበረች ፡ አገርንም ፡ ከወረሱ ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ ተካፋይ ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ ይወድሃል ።
፲፬፤ ቢታገሡኝ ፡ መወደድንና ፡ ክብርን ፡ አወርሳቸዋለሁ ፡ ብፁዓልና ፡ ጸሎት ፡ በሚጸለይበት ፡ በቤተ ፡ መቅደስ ፡ ደስ ፡ አሰኘቸዋለሁና ፡ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ መሥዋዕት ፡ የተወደዱና ፡ የተመረጡንም ፡ ይሆናሉ ፡ ብፁዓልና ።
፲፭፤ ከሞት ፡ ወደ ፡ ሕይወት ፡ ትሻገሩ ፡ ዘንድ ፡ ድኅነታችሁ ፡ በሚደረግበት ፡ ሥራንና ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ ማድረግን ፡ ቸል ፡ አትበሉ ።
፲፮፤ በጎ ፡ ሥራ ፡ የሚሠሩ ፡ ሰዎችን ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ከመከራው ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ጠበቀው ፡ እንደ ፡ ኢዮብ ፡ ባሮቹን ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ በበጎ ፡ ሥራው ፡ ሁሉ ፡ ይጠብቃቸዋል ።
፲፯፤ ነገሥታቱን ፡ በገደላቸው ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ አዳነው ፡ እንደ ፡ አብርሃም ፡ ጣዖት ፡ ያስመለኩት ፡ ዘንድ ፡ ማታና ፡ ጧት ፡ ሌትና ፡ ቀን ፡ ሰውነቱንም ፡ ሲያውኳት ፡ ከነበሩ ፡ አብርሃም ፡ ከኖረባቸው ፡ ከከናኔዎን ፡ እጅና ፡ ከፈርዖን ፡ እጅ ፡ እንዳዳነው ፡ እንደ ፡ ሙሴም ፡ ባሮቹ ፡ ይሆኑት ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ በበጎ ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ይጠብቃቸዋል ።
፲፰፤ እሱ ፡ ግን ፡ የሳቸው ፡ ገንዘብ ፡ ወደ ፡ ሆኑ ፡ ወደ ፡ ጣዖታቱ ፡ ሲወስዱት ፡ እምቢ ፡ እያለ ፡ መከራውን ፡ ይታገሥ ፡ ነበረ ።
፲፱፤ ከልጅነቱ ፡ ጀምሮ ፡ እሱን ፡ ያመነው ፡ አብርሃም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ የታመነ ፡ ወዳጁ ፡ ነበርና ፡ እሱም ፡ እምቢ ፡ እያለ ፡ የፈጠረው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያመልከው ፡ ነበረ ።
፳፤ እግዚአብሔርን ፡ ፈጽሞ ፡ ይወደዋልና ፡ እስኪሞት ፡ ድረስ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ማምለክ ፡ አልተወውም ፡ እስከሚሞትበትም ፡ ድረስ ፡ ከሕጉም ፡ አልወጣም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ፡ ልጆቹንም ፡ አስተማረ ።
፳፩፤ አባታቸው ፡ አብርሃም ፡ ሕጉን ፡ እንደ ፡ ጠበቀ ፡ እነሳቸውም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ አልወጡም ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ አብርሃም ፡ የሚባል ፡

ወዳጅ ፡ አለኝ ፡ ብሎ ፡ ለመላእክት ፡ እንደ ፡ ነገ
ራቸው ፡ እግዚአብሔር ፡ ስለነሳቸው ፡ የተና
ገረ ፡ ብሮቹ ፡ የሚሆኑ ፡ የአብርሃም ፡ ልጆች ፡
ያዕቆብና ፡ ይስሐቅ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡
አልወጡም ።
፳፪ በነሳቸው ፡ ዘንድ ፡ የተመሰገነ ፡ ሁሉን ፡ የሚ
ገዛ ፡ እግዚአብሔር ፡ አብርሃም ፡ ወዳጄ ፡ ነው ፡
ይስሐቅ ፡ በለሚሴ ፡ ነው ፡ ያዕቆብም ፡ ልቡናዬ ፡
የወደደችው ፡ ወዳጄ ፡ ነው ፡ አለ ።
፳፫ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ፈጽሞ ፡ ሲወዳቸው ፡
እነሳቸው ፡ ግን ፡ ዘወትር ፡ ሲያሳዝኑት ፡ ኖሩ ፡
እሱም ፡ ሲታገሣቸው ፡ በምድረ ፡ በዳም ፡ መና ፡
ሲመግባቸው ፡ ኖረ ።
፳፬ ልብሳቸው ፡ አላረጀም ፡ የውቀት ፡ እንጀራ ፡
የሚሆን ፡ መናን ፡ ተመግበዋልና ፡ እግራቸ
ውም ፡ አልነቃም ።
፳፭ ልቡናቸው ፡ ግን ፡ ሁልጊዜ ፡ ከእግዚአብሔር ፡
ይርቅ ፡ ነበር ፡ ከጥንት ፡ጀምሮ ፡ ኃጢአት ፡ የሚ
ሠሩ ፡ ነበሩና ፡ ለመዳን ፡ ተስፋ ፡ አልነበራቸ
ውም ።
፳፮ እንደ ፡ ጠማማ ፡ ቀስት ፡ ሆኑ ፡ እንጂ ፡ በማረ ፡
አነዋወራቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንዳገለገ
ሉት ፡ እንደ ፡ አባቶቻቸው ፡ እንደ ፡ ይስሐቅና ፡
እንደ ፡ አብርሃም ፡ እንደ ፡ ያዕቆብም ፡ አልሆ
ኑም ፡ በተራራውና ፡ በኮረፍታው ፡ ላይ ፡ በሉ ፡
ጣዖቶቻቸው ፡ ሁልጊዜ ፡ ያሳዝኑት ፡ ነበር ፡ በተ
ራራው ፡ ላይ ፡ በዋሻውና ፡ በዛፎቹም ፡ ሥር ፡
ይበሉ ፡ ነበር ።
፳፯ ፍሪዳ ፡ ያርዱ ፡ ነበር ፡ መሥዋዕት ፡ ይሠዉ ፡
ነበር ፡ በእጃቸውም ፡ ሥራ ፡ ደስ ፡ ይላቸው ፡
ነበር ፡ ተረፈ ፡ መሥዋዕቱን ፡ ይበሉ ፡ ነበር ፡ የመ
ሥዋዕታቸውን ፡ ይጠጡ ፡ ነበር ፡ እየዘፈኑም ፡
ከአጋንንት ፡ ጋራ ፡ ይጫወቱ ፡ ነበር ።
፳፰ አጋንንትም ፡ ጨዋታቸውንና ፡ ዘፈናቸውን ፡
ሁሉ ፡ ያደንቁላቸው ፡ ነበር ፡ ስካራቸውንም ፡
ያለልክም ፡ ዝሙትን ፡ ይሠሩ ፡ ነበር ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ የማይወደው ፡ ቅሚያና ፡ ስስትንም ፡
ያደርጉ ፡ ነበር ።
፳፱ ለከነዓን ፡ ጣዖት ፡ ለምድያም ፡ ጣዖትና ፡ ለበዓ
ልም ፡ የኤሎፍሊ ፡ ጣዖቶች ፡ ለሚሆኑ ፡ ለአጵ
ሎንና ፡ ለዳጎንም ፡ ለሰራጽዮንና ፡ ለአርጤማ
ዴስም ።
፴ በዙሪያቸው ፡ ላሉ ፡ ለአሕዛብም ፡ ጣዖታት ፡
ሁሉ ፡ መሥዋዕት ፡ ይሠዉ ፡ ነበር ፤ ባዩ ፡ በሰሙ ፡
ገንዘብ ፡ አሕዛብ ፡ ጣዖት ፡ እንዲያመልኩ ፡ እስ
ራኤልም ፡ ሁሉ ፡ ጣዖት ፡ ያመልኩ ፡ ነበር ፡ ጨዋ
ታቸውንና ፡ ዘፈናቸውን ፡ አሕዛብም ፡ የሚያደ
ርጉት ፡ ድንፋታቸውን ፡ ያደርጉ ፡ ነበር ።
፴፩ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ፡ ጣዖ
ትንም ፡ ከማምለክ ፡ ይርቁ ፡ ዘንድ ፡ ሙሴ ፡ በአ
ሪት ፡ የነገራቸው ፡ ትእዛዙንና ፡ ሕጉን ፡ ሳይጠ
ብቁ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እናመልከዋለን ፡ የሚሉ ፡
የእስራኤል ፡ ወገን ፡ ሁሉ ፡ እንደዚሁ ፡ ያደር
ጋሉ ።

የኩዳዱን ፡ እህል ፡ ከመገባቸው ፡ ወደ ፡ ምድ ፴፪
ሩም ፡ አገዝመራ ፡ ከወጣቸው ፡ ከማጋ ፡ የተገኘ ፡
ማሩንም ፡ የመገባቸው ፡ መናውንም ፡ የመገባ
ቸው ፡ ከባቶቻቸው ፡ ፈጣሪ ፡ በቀር ፡ የተለዩ ፡
ጣዖታትን ፡ እንዳያመልኩ ።
ሙሴ ፡ አታምልኩ ፡ ብሎ ፡ አዘዛቸው ፡ ፈጣሪያ ፴፫
ቸው ፡ ነውና ፡ የወደዱትንም ፡ ይመግባቸዋልና ፡
የወደዱትን ፡ የተመኙትንም ፡ አላሳጣቸውም ።
እነሱቸው ፡ ግን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ማሳዘን ፡ አል ፴፬
ተዉም ፡ ደስም ፡ በሰኛቸው ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብ
ሔርን ፡ ያሳዝኑት ፡ ነበር ።
በሳዘናቸውም ፡ ጊዜ ፡ ወደሱ ፡ ይጮሁ ፡ ነበር ፡ ፴፭
ከገኛቸውም ፡ መከራ ፡ ያድናቸው ፡ ነበር ፡ ዳግ
መኛም ፡ ፈጽሞ ፡ ደስ ፡ ይላቸው ፡ ነበር ፡ ብዙ ፡
ዘመንም ፡ ይኖሩ ፡ ነበር ።
እንደ ፡ ቀድሞው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያሳዝኑት ፡ ፴፮
ዘንድ ፡ የዚያን ፡ ጊዜም ፡ ፈጽመው ፡ ልባቸውን ፡
ወደ ፡ ኃጢአት ፡ ይመልሱ ፡ ነበር ፡ ያጠኙቸው ፡
ዘንድ ፡ በዙሪያቸው ፡ ያሉ ፡ አሕዛብንም ፡ ያስነ
ሣባቸው ፡ ነበር ፡ አስጨንቀውም ፡ ያስገብሩዋ
ቸው ፡ ነበር ።
ዳግመኛም ፡ ፈጽመው ፡ ተመልሰው ፡ ወደ ፡ ፈጣ ፴፯
ሪያቸው ፡ ወደ ፡ እግዚአሔር ፡ ይጮሁ ፡ ነበር ።
እሱም ፡ ይቅር ፡ ይላቸው ፡ ነበር ፡ በማረ ፡ አነዋ ፴፰
ወራቸው ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ እግዚአብሔርን ፡
ስለ ፡ አገለገሉት ፡ መሐላውን ፡ ስለ ፡ አጸናላ
ቸው ፡ ስለ ፡ አባቶቻቸው ፡ ስለ ፡ ኖኅ ፡ ስለ ፡ ይስ
ሐቅና ፡ ስለ ፡ አብርሃም ፡ ስለ ፡ ያዕቆብም ፡ ነው ፡
እንጂ ፡ ይቅር ፡ የሚላቸው ፡ ስለ ፡ ራሳቸው ፡
ሥራ ፡ አይደለም ።
እንደ ፡ ሰማይ ፡ ከዋክብትና ፡ እንደ ፡ ባሕር ፡ ፴፱
አሸዋ ፡ ልጆቻቸውን ፡ ያበዛ ፡ ዘንድ ፡ ወደው ፡
ሕጉን ፡ የጠበቁ ፡ ሰዎችንም ፡ ወደዳቸው ።
እንደ ፡ ባሕር ፡ አሸዋ ፡ ያላቸው ፡ ግን ፡ ሙታን ፡ ፵
በተነሡ ፡ ጊዜ ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ተለይ
ተው ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡ የሚገቡ ፡ የኃጢአተኞች ፡
ሰዎች ፡ ነፍሳት ፡ ናቸው ።
እግዚአብሔር ፡ አብርሃምን ፡ ሌሊት ፡ ወደ ፡ ፵፩
ሰማይ ፡ እይ ፡ መቍጠርም ፡ ትችል ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
የሰማይን ፡ ከዋክብት ፡ ቍጠራቸው ፡ ብሎታ
ልና ፡ እንደዚሁ ፡ ልጆችህ ፡ ጻድቃንም ፡ እንደ ፡
ሰማይ ፡ ከዋክብት ፡ በመንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ ያበ
ራሉ ፡ ብሎታልና ፡ በሰማይ ፡ ላይ ፡ እንደሚያ
በሩ ፡ ከዋክብት ፡ ናቸው ፡ ያላቸው ፡ ግን ፡ ከእስ
ራኤል ፡ የተወለዱ ፡ የደጋጎች ፡ ሰዎች ፡ ነፍሳት ፡
ናቸው ።
ዳግመኛም ፡ ወደ ፡ ወንዙ ፡ ዳርቻና ፡ ወደ ፡ ባሕሩ ፡ ፵፪
አስተውል ፡ ባሸዋው ፡ መካከል ፡ ያለውንም ፡
እይ ፡ መቍጠር ፡ ትችል ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ቍጠር ፡
ሙታን ፡ በተነሡ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡ የሚወ
ርዱ ፡ ኃጢአተኞች ፡ ልጆችህም ፡ እንደዚሁ ፡
ናቸው ፡ ብሎታልና ፡ የኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡
ነፍሳት ፡ ናቸው ።
አብርሃምም ፡ በእግዚአብሔር ፡ አመነ ፡ ስለዚህ ፡ ፵፫

ነገር ፡ እውነት ፡ ሆኖ ፡ ተቈጠረለት ፡ በዚህ ፡
ዓለም ፡ አለኝታውን ፡ አገኘ ፡ ሚስቱ ፡ ሳራም ፡
ካረጀች ፡ በኋላ ፡ ይስሐቅ ፡ የሚባል ፡ ልጅን ፡
ወለደች ።
፴፬ ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ የሠሩ ፡ ሰዎች ፡ ተነሥተው ፡ ዘለዓ
ለም ፡ ጸንቶ ፡ ወደሚኖር ፡ ወደ ፡ መንግሥተ ፡
ሰማያት ፡ እንዲሔዱ ፡ አምኗልና ፡ ዳግመኛም ፡
በሰማይ ፡ መንግሥትን ፡ ያገኛል ።
፴፭ ፡ ኃጢአትን ፡ የሠሩ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ሙታን ፡ በተ
ነሡ ፡ ጊዜ ፡ ለዘለዓለም ፡ ጸንቶ ፡ ወደሚኖር ፡
ወደ ፡ ገሃነም ፡ እንዲሔዱ ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ የሠሩ ፡
ጻድቃን ፡ ግን ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ እንዲ
ነግሡ ፡ አምኗልና ።
ኃጢአት ፡ በሠሩ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ በውነት ፡ ያለ ፡ ፴፮ ፡
ሐሰት ፡ ለዘዓለሙ ፡ እንዲፈረድባቸው ፡ አምኗ
ልና ፡ በሰማይ ፡ የሕይወት ፡ መንግሥት ፡ ያገኛልና ።
በውነት ፡ ያለ ፡ ሐሰት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ክብ
ርና ፡ ምስጋና ፡ ይግባውና ፡ የመቃብያንን ፡
ነገር ፡ የሚናገር ፡ መጀመሪያው ፡ መጽሐፍ ፡
መላ ፡ ተፈጸመ ።

# መጽሐፈ ፡ መቃብያን ፡ ካልዕ ።

ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ መቃቢስ ፡ እስራኤልን ፡ የሶርያ ፡ ክፍል ፡
በምትሆን ፡ በመስጴጦምያ ፡ አግኝቶ ፡ ከኢያ
ቡቅ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ አደባባይ ፡
ድረስ ፡ በውራጃቸው ፡ እንደ ፡ ገደላቸው ፡ የከ
በረች ፡ አገርንም ፡ እንዳጠፋት ፡ የሚናገር ፡
መጽሐፍ ፡ ይህ ፡ ነው ።
፪፤ የሶርያና ፡ የኤዶምያስ ፡ ሰዎች ፡ አማሌቃውያ
ንም ፡ የኢየሩሳሌምን ፡ አገር ፡ ካጠፉ ፡ ከምዓቡ ፡
ሰው ፡ ከመቃቢስ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፡ ከሰ
ማርያ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ አደባባይ ፡
ድረስ ፡ እስከ ፡ አውራጃዋም ፡ ሁሉ ፡ ድረስ ፡
ሰፍረዋልና ፡ ከጥቂቶች ፡ ሰዎች ፡ በቀር ፡ የሚ
ሸሽ ፡ ሰው ፡ ሳያስቀሩ ፡ በጦር ፡ ገደሉ ።
፫፤ የእስራኤልም ፡ ልጆች ፡ በበደሉ ፡ ጊዜ ፡ የሞ
ዓብ ፡ ሰው ፡ መቃቢስን ፡ አስነሣባቸው ፡ እሱም ፡
በሰይፍ ፡ ገደላቸው ።
፬፤ ስለዚህም ፡ ነገር ፡ የእግዚአብሔር ፡ ጠላቶች ፡
አሕዛብ ፡ በከበረች ፡ አገሩ ፡ ላይ ፡ ደነፉ ፡ በወን
ጀላቸውም ፡ ተማማሉ ።
፭፤ የኢሎፍሊና ፡ የኢዶምያስም ፡ ሰዎች ፡ ሰፈሩ ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስለ ፡ ተገዳደሩ ፡ እሱ ፡
ልኳቸዋልና ፡ የእግዚአብሔርን ፡ አገር ፡ ተበቅ
ለው ፡ ያጠፉ ፡ ጀመሩ ።
፮፤ የዚያም ፡ የመቃቢስ ፡ አገሩ ፡ የሞዓብ ፡ ክፍል ፡
የምትሆን ፡ ሬማት ፡ ናት ፡ ከሀገሩም ፡ በኃይል ፡
ተነሥቶ ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ ካሉ ፡ ሰዎችም ፡ ጋራ ፡
ተማማሉ ።
፯፤ የእግዚአብሔርንም ፡ አገር ፡ ያጠፉ ፡ ዘንድ ፡
የመስጴጦምያ ፡ ዕፃ ፡ በምትሆን ፡ በጌላቡሄ ፡
አውኛራ ፡ እስከ ፡ ሶርያ ፡ ድረስ ፡ ሰፈሩ ፡ በዚ
ያም ፡ አማሌቃውያንና ፡ ኢሎፍላውያንን ፡
ለመነ ፡ በወንጀል ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ይሆኑ ፡
ዘንድ ፡ ብዙ ፡ ብርና ፡ ወርቅን ፡ ሠረገላዎችና ፡
ፈረሶችንም ፡ ሰጣቸው ።
፰፤ አንድነት ፡ መጥተው ፡ አምባዪቱንም ፡ ናዷት ፡
በሷ ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ደምን ፡ እንደ ፡ ውሀ ፡
አፈሰሱ ።
ኢየሩሳሌምንም ፡ እንደ ፡ ተክል ፡ ጠባቂ ፡ ጎጆ ፡ ፱፤
አደረጓት ፡ በውስጧም ፡ ድምፅ ፡ አሰማበት ፡
እግዚአብሔር ፡ የማይወደው ፡ የኃጢአትን ፡
ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ሠራ ፡ ምስጋናና ፡ ክብርንም ፡ የተ
መላች ፡ የእግዚአብሔር ፡ አገርንም ፡ አረከሱ ።
የወዳጆችህን ፡ ሥጋና ፡ የባሮችህን ፡ እሬሳ ፡ ለም ፲፤
ድረ ፡ በዳ ፡ አውሬዎችና ፡ ለሰማይ ፡ ወፎች ፡
ምግብ ፡ አደረጉ ።
እናት ፡ አባቱ ፡ የሞቱበት ፡ ልጅንና ፡ ባልቴት ፲፩፤
ንም ፡ ቀሙ ፡ ሰይጣን ፡ እንዳስተማራቸው ፡ እግ
ዚአብሔርን ፡ ሳይፈሩ ፡ አድርገዋልና ፡ ኩላሊ
ትና ፡ ልቡና ፡ የሚመረምር ፡ እግዚአብሔር ፡
እስኪቈጣ ፡ ድረስ ፡ በፀነሱ ፡ ሴቶች ፡ ሆድ ፡ ያለ
ውንም ፡ ፅንስ ፡ አወጡ ።
በእግዚአብሔር ፡ ወገኖች ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ሥራን ፡ ፲፪፤
ስለ ፡ ሠሩ ፡ ደስ ፡ እያላቸው ፡ ወደ ፡ አገራቸው ፡
ተመለሱ ፡ ከከበረች ፡ አገር ፡ የማረኩትንም ፡
ምርኮ ፡ ወሰዱ ።
ተመልሰው ፡ ወደቤታቸው ፡ በገቡ ፡ ጊዜ ፡ ደስ ፲፫፤
ታን ፡ ዘፈንና ፡ ጭብጨባንም ፡ አደረጉ ።

ምዕራፍ ፡ ፪ ።

ረዓይ ፡ የሚሉት ፡ ነቢይ ፡ እንዲህ ፡ አለው ፡ ፩፤
ተድላ ፡ ደስታ ፡ በሚደረግበት ፡ ጊዜ ፡ ዛሬ ፡
ጥቂት ፡ ደስ ፡ ይበልህ ፡ እስራኤል ፡ ያከበሩት ፡
እግዚአብሔር ፡ ባልተጠራጠርከው ፡ መቅሠ
ፍት ፡ ተበቅሎ ፡ ያጠፋህ ፡ ዘንድ ፡ አለው ።
ፈረሶቹ ፡ ፈጣኖች ፡ ናቸው ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ፪፤
በሩጫ ፡ አመልጣለሁ ፡ ትላለህን ።
እኔስ ፡ የሚከተሉህ ፡ ሰዎች ፡ ከአሞሮች ፡ ይፈ ፫፤
ጥናሉ ፡ ከሚመጣብህ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ፍር
ድና ፡ ከጥፋት ፡ አታመልጥም ፡ እልሃለሁ ።
የብረት ፡ ልብስ ፡ እለብሳለሁ ፡ የጦር ፡ መወርወ ፬፤
ርና ፡ የቀስትም ፡ መንደፍ ፡ አይችለኝም ፡ ትላለ
ህን ፤ እስራኤልን ፡ የሚከብር ፡ እግዚአብሔር ፡
ተበቅዬ ፡ እማጠፋህ ፡ በጦር ፡ መወርወር ፡ አይደ
ለም ፡ አለ ፡ አለው ፡ ከጦር ፡ መወርወርና ፡ ከቀ
ስት ፡ ንድፈት ፡ የሚከፋ ፡ ጽኑ ፡ የሆነ ፡ የልብ ፡
በሽታን ፡ እከክና ፡ የቁርጥማት ፡ በሽታንም ፡

አመጣብሃለሁ ፡ እንጂ ፡ ተበቅዬ ፡ የማጠፋህ ፡
በዚህ ፡ አይደለም ።
፭፤ ቍጣየን ፡ እነግሥተሃል ፡ የልብ ፡ በሽታን ፡ አመጣ
ብሃለሁ ፡ የሚረዳህም ፡ ታጣለህ ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡
ስም ፡ አጠራርህን ፡ እስከጠፋው ፡ ድረስ ፡ ከሥ
ልጣኔም ፡ አታመልጥም ።
፮፤ ክማደ ፡ ልቡናህን ፡ አጽንተሃልና ፡ ራስህን ፡
በገሬ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አድርገሃልና ፡ ይኸንን ፡ ነገር ፡
እንደ ፡ ዓይን ፡ ጥቅሽ ፡ ፈጥኜ ፡ በደረግሁ ፡ ጊዜ ፡
እኔ ፡ ፈጣሪህ ፡ እንደሆንሁ ፡ ታውቀኛለህ ፡
አንተ ፡ በፊቱ ፡ እሳት ፡ እንደሚበላው ፡ በነፋስ ፡
ፊት ፡ እንዳለ ፡ ሣር ፡ ነህና ፡ ነፋሳት ፡ ከምድር ፡
አፍሰው ፡ እንደሚበትኑትም ፡ ትቢያ ፡ ነህና ፡
አንተ ፡ በኔ ፡ ዘንድ ፡ እንደነሱ ፡ ነህ ።
፯፤ ቍጣየን ፡ እነግሥተሃልና ፡ ፈጣሪህንም ፡ አላወ
ቅህምና ፡ እኔም ፡ ወገንህን ፡ ሁሉ ፡ ቸል ፡ እለዋ
ለሁ ፡ በምበህም ፡ ላይ ፡ የተጠጋውንም ፡ አላስ
ቀርም ።
፰፤ አሁንም ፡ ከሠራኸው ፡ ኃጢአትህ ፡ ሁሉ ፡ ተመ
ለስ ፡ ከኃጢአትህ ፡ ተመልሰህ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ፈጽመህ ፡ በልቅሶና ፡ በኀዘን ፡ ብትለማ
መጥ ፡ በንጹሕ ፡ ልቡናም ፡ ወደሱ ፡ ብትለምን ፡
በፊቱ ፡ የሠራኸውን ፡ ኃጢአትህን ፡ ሁሉ ፡ እግ
ዚብብሔር ፡ ይቅር ፡ ይልሃል ፡ አለው ።
፱፤ እግዚአብሔር ፡ ተቈጥቶታልና ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡
መቃቢስ ፡ ትቢያ ፡ ለብሶ ፡ ስለ ፡ ኃጢአቱ ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ አለቀሰ ።
፲፤ ዓይኖቹ ፡ የተገለጡ ፡ ናቸውና ፡ አያስቀርምና ፡
ገሮዋውም ፡ የተከፈተ ፡ ነውና ፡ ቸል ፡ አይል
ምና ፡ የተናገረውንም ፡ ቃል ፡ ሐሰት ፡ አያደር
ግምና ፡ በንዲት ፡ ጊዜም ፡ ፈጥኖ ፡ ያደርጋቃ
ልና ፡ እግዚአብሔር ፡ በነቢዩ ፡ ቃል ፡ የተናገረ
ውን ፡ መቅሠፍት ፡ እንዳያስቀር ፡ አወቀና ።
፲፩፤ ልብሱን ፡ ጥሎ ፡ ማቅ ፡ ለበሰ ፡ በራሱም ፡ ላይ ፡
ትቢያ ፡ ነሰነሰ ፡ ስለ ፡ ሠራው ፡ ኃጢአቱም ፡
በፈጣሪው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ጮኸ ፡
አለቀሰ ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩፤ የሞዓብ ፡ ክፍል ፡ የምትሆን ፡ ሬማት ፡ ለሰርያ ፡
ቅርብ ፡ ናትና ፡ ነቢዩም ፡ ከሬማት ፡ መጥቶ ፡
ነገረው ።
፪፤ ጕድጓድ ፡ ቆፍሮ ፡ እስከ ፡ አንገቱ ፡ ድረስ ፡ ገብቶ ፡
ጽኑዕ ፡ ዕንባን ፡ አለቀሰ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
ስለ ፡ ሠራው ፡ ኃጢአቱም ፡ ንስሐ ፡ ገባ ።
፫፤ እግዚአብሔርም ፡ ነቢዩን ፡ እንዲህ ፡ አለው ፡
ከይሁዳ ፡ አገር ፡ ከሬማት ፡ ወደ ፡ ሞዓቡ ፡ ሹም ፡
ወደ ፡ መቃቢስ ፡ ተመለስ ፡ አለው ። እግዚአብ
ሔር ፡ እንዲህ ፡ አለህ ፡ በለው ፡ በኃይሉ ፡ ጽናት ፡
በሠራዊቱ ፡ ብዛት ፡ የከበረች ፡ አገር ፡ ኢየሩሳ
ሌምን ፡ አጠፋኋት ፡ እንድትል ፡ አገሬን ፡ ታጠፋ ፡
ዘንድ ፡ ያንተ ፡ ፈጣሪ ፡ የምሆን ፡ እኔ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ በፈቃዴ ፡ ሰደድኩህ ፡ እንጂ ፡ ይህንን ፡
ነገር ፡ ያደረግኸው ፡ አንተ ፡ አይደለህም ፡ አለህ ፡
በለው ።
በስስቷ ፡ ሁሉ ፡ በክዳቷና ፡ በሴሰኝነቷም ፡ አሳ ፬፤
ዝናኛለችና ።
እኔም ፡ ቸል ፡ ብዬ ፡ በንተ ፡ እጅ ፡ ጣልኋት ፡ ፭፤
አሁንም ፡ ስለ ፡ ወለድሆቸው ፡ ልጆችህ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ኃጢአትህን ፡ ይቅር ፡ አለህ ፤ ክማደ ፡
ልቡናህን ፡ ስላጸናህ ፡ በሥልጣኔም ፡ ጽናት ፡
አገሬቱን ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ ከበብኋት ፡ ስለምትል ፡
ስለ ፡ አንተ ፡ አይደለም ።
የሚጠራጠሩ ፡ ሰዎች ፡ ንስሐ ፡ ለመግባት ፡ አይ ፮፤
ጨክኑምና ፡ ተጠራጣሪ ፡ አትሁን ፡ አሁንም ፡
በፍጹም ፡ ልቡናህ ፡ ጨክነህ ፡ ንስሐ ፡ ግባ ።
ነገር ፡ ግን ፡ በፍጹም ፡ ልቡናቸው ፡ ንስሐ ፡ የሚ ፯፤
ገቡ ፡ ስለ ፡ ኃጢአታቸው ፡ ንስሐ ፡ በገቡበት ፡
ሁሉ ፡ ዳግመኛም ፡ ወደ ፡ ጥመት ፡ ወደ ፡ ኃጢ
አት ፡ የማይመለሱ ፡ ሰዎች ፡ የተደነቁ ፡ ናቸው ።
በልቅሶና ፡ በኀዘን ፡ በስግደትና ፡ በብዙ ፡ ልመና ፡ ፰፤
ጨክነው ፡ ወደ ፡ ፈጣሪያቸው ፡ ወደ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ የሚመለሱ ፡ ሰዎች ፡ የተደነቁ ፡ ናቸው ።
ንስሐ ፡ የገቡን ፡ ሰዎች ፡ ካሳታችሁ ፡ በኋላ ፡
ንስሐ ፡ የገባችሁ ፡ እናንተ ፡ የኔ ፡ ገንዘቦች ፡
ናችሁ ፡ ብሏቸዋልና ፡ ጨክነው ፡ ንስሐ ፡ የሚ
ገቡ ፡ ሰዎች ፡ የተደነቁ ፡ ናቸው ።
ትቢተኛ ፡ መቃቢስን ፡ ካሳተ ፡ በኋላ ፡ በንስሐ ፡ ፱፤
ወደሱ ፡ በተመለሰ ፡ ጊዜ ፡ ስለ ፡ ፍርሃትህና ፡
ስለ ፡ ድንጋፄህ ፡ ኃጢአትህን ፡ ይቅር ፡ እልሃለሁ ፡
አለው ፤ በባት ፡ ኃጢአት ፡ እስከ ፡ ሰባት ፡ ትው
ልድ ፡ ድረስ ፡ በልጆች ፡ ፍዳ ፡ የማመጣ ፡ አባቱ ፡
የሠራውን ፡ ኃጢአት ፡ ልጁ ፡ ቢሠራ ፡ ለሚወ
ዱኝ ፡ ሕጌንም ፡ ለሚጠብቁ ፡ ሰዎች ፡ ለነሳቸው ፡
እስከ ፡ እልፍ ፡ ትውልድ ፡ ድረስ ፡ ቸርነትን ፡
የማደርግ ፡ ፈጣሪህ ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝና ።
አሁንም ፡ ስለ ፡ ወለድኻቸው ፡ ስለነዚህ ፡ ልጆ ፲፤
ችህ ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ መሐላዬን ፡ አጸናለሁ ፡
ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ እስራኤልን ፡ ያከበረ ፡ እግዚ
አብሔርም ፡ ስለ ፡ ሠራኸው ፡ ኃጢአትህ ፡ ያደ
ረግኸውን ፡ ንስሐ ፡ እቀበላለሁ ፡ አለ ።
የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ከጕድጓዱ ፡ ወጥቶ ፡ ለነቢዩ ፡ ፲፩፤
ሰገደ ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አሳዝኜዋለሁና ፡
የወደድኸውን ፡ አድርገኝ ፡ እንጂ ፡ ካንተ ፡ እን
ዳልለይ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ እንዲህ ፡ ያድ
ርገኝ ፡ ብሎ ፡ ማለ ፡ ለኛ ፡ ሕግ ፡ የለንምና ፡ እንዳ
ባቶቼ ፡ በትእዛዙ ፡ ጸንቼ ፡ አልኖርሁም ፡ አባቶ
ቻችን ፡ እንዳስተማሩን ፡ ጣዖትም ፡ እንድናመ
ልክ ፡ አንተ ፡ ታውቃለህ ።
በኃጢአቱ ፡ ጸንቼ ፡ የኖርሁ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ፲፪፤
ትእዛዝ ፡ ባሳዘንሁበት ፡ በክማደ ፡ ልቡናዬ ፡
ጽናትና ፡ በልቡናዬ ፡ ትቢት ፡ የጸናሁ ፡ ኃጢአ
ተኛ ፡ ነኝና ፡ እኔ ፡ ግን ፡ እስካሁን ፡ ድረስ ፡ የእ
ግዚአብሔር ፡ አገልጋዮች ፡ የነቢያት ፡ ቃልን ፡
አልሰማሁም ፡ ነበር ፡ ባዘዙኝም ፡ በሕጉና ፡ በትእ
ዛዙ ፡ ጸንቼ ፡ አልኖርሁም ።
ከናንተ ፡ አስቀድሞ ፡ ከወገናችሁ ፡ ኃጢአቱን ፡ ፲፫፤
የታመነ ፡ የለምና ፡ ነቢዩ ፡ ዛሬ ፡ ንስሐን ፡ እንደ ፡

ተቀበለ ፡ አወቀሁ ፡ ብሎ ፡ ነገረው ።
፲፬ አሁን ፡ ግን ፡ ጣዖት ፡ ማምለክህን ፡ ትተህ ፡ እው
ነተኛ ፡ ንስሐን ፡ ይሆንህ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔ
ርን ፡ ወደ ፡ ማወቅ ፡ ተመለስ ፡ አለው ፡ በነቢዩ ፡
እግር ፡ ወድቆ ፡ ሰገደ ፡ ነቢዩም ፡ እንሥቶ ፡ የሚ
ገባውን ፡ በጎ ፡ ሥራውን ፡ ሁሉ ፡ አዘዘው ።
፲፭ እግዚአብሔርም ፡ እንዳዘዘውም ፡ አድርጎ ፡ ወደ ፡
ቤቱ ፡ ተመለሰ ።
፲፮ ያም ፡ መቃቢስ ፡ ሰውነቱን ፡ እግዚአብሔርን ፡
ወደ ፡ ማምለክ ፡ መለሳት ፡ ከቤቱም ፡ ጣዖቱንና ፡
ጥንቈላውንም ፡ ጣዖት ፡ የሚያመልኩ ፡ ሰዎች
ንና ፡ ሟርተኞችን ፡ ጠንቋዮችንም ፡ አጠፋ ።
፲፯ ከኢየሩሳሌም ፡ ማርኮ ፡ ያመጣቸውን ፡ ልጆች ፡
አባቶቻቸው ፡ እንደሚያደርጉ ፡ የእግዚአብሔ
ርን ፡ ትእዛዝ ፡ ሁሉ ፡ ሥራቱንና ፡ ሕጉንም ፡
ጢትና ፡ ማታ ፡ ይመረምሩቸው ፡ ነበር ።
፲፰ ከተማረኩትም ፡ ልጆች ፡ አዋቆችን ፡ በቤቱ ፡
ሾመ ።
፲፱ ዳግመኛም ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ የሚያደር
ጉትን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ ያስተምሯ
ቸው ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ መኝታው ፡ የሚገቡ ፡ ታና
ናሽ ፡ የሆኑ ፡ የተደላደሉ ፡ ልጆችን ፡ የሚጠ
ብቁ ፡ አዋቆች ፡ ልጆችን ፡ ከሕፃናቱ ፡ ሾመ ፡
ሥራቱንና ፡ ሕጉን ፡ አምልኮቱንና ፡ ዘጠኙንም ፡
ሕገጋት ፡ የሞዓብ ፡ ሰዎች ፡ ሥራት ፡ የሚያደ
ርጉትም ፡ ምስጊዳቸውን ፡ ከንቱ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
ከተማረኩ ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ይሰማ ፡ ነበር ።
፳ ምስጊዳቸውን ፡ ጣዖታቸውንና ፡ ጥንቈላቸ
ውን ፡ ጢትና ፡ ማታ ፡ ከፍየሎቹ ፡ ጠቦቶችና ፡
የሰቡ ፡ ከሆኑ ፡ ከበጎቹ ፡ መንጋዎች ፡ ለጣዖታቱ ፡
የሚሠዋውን ፡ መሥዋዕቱንና ፡ ወይኑንም ፡
አጠፋ ።
፳፩ በሰዓትና ፡ በቀትር ፡ መሥዋዕት ፡ እየሠዋ ፡ በሥ
ራው ፡ ሁሉ ፡ የሚያመልካቸውን ፡ የሚለምና
ቸውን ፡ የሚያምናቸውን ፡ የጣዖታቱንም ፡ ካህ
ናት ፡ ለነገሩትም ፡ ሁሉ ፡ ፈቃዳቸውንም ፡ የሚ
ያደርግላቸው ፡ ጣዖታቱን ፡ አጠፋ ።
፳፪ በነገሩ ፡ ሁሉ ፡ የሚያድኑት ፡ ይመስለው ፡ ነበ
ርና ፡ የነገሩትን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ አይንቅም ፡ ነበር ።
፳፫ ያ ፡ መቃቢስ ፡ ግን ፡ የነሳቸውን ፡ ሥራ ፡ ተወ ።
፳፬ ነቢይ ፡ የሚሉት ፡ የራዓዩን ፡ ነገር ፡ ከሰማው ፡
በኋላ ፡ በንስሐ ፡ ሥራውን ፡ አከናወነ ፡ የእስራ
ኤል ፡ ልጆች ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ያሳዝኑት ፡ ነበርና ፡
በመከራውም ፡ በቀሠፋቸው ፡ ጊዜ ፡ አውቀው ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ይጮሃሉና ፡ ወገኖቹ ፡
ሁሉ ፡ በዚያ ፡ ወራት ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡
ይልቅ ፡ በጎ ፡ ሥራን ፡ ሠሩ ።
፳፭ መከራ ፡ በሚያጸኑባቸው ፡ በአሕዛብ ፡ እጅ ፡
ተይዘው ፡ እንደ ፡ ጐስቈሉ ፡ ወደሱ ፡ እንደ ፡
ጮሁ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ያባቶቻቸውን ፡ መሐላ ፡
አስቦ ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ስለ ፡ አባቶቻቸው ፡ ስለ ፡
ይስሐቅ ፡ ስለ ፡ አብርሃም ፡ ስለ ፡ ያዕቆብም ፡
ይቅር ፡ ይላቸው ፡ ነበር ።
፳፮ ባዳናቸውም ፡ ጊዜ ፡ ከመከራ ፡ ያዳናቸው ፡ እግ
ዚአብሔርን ፡ ይረሱት ፡ ነበር ፡ ጣዖቱንም ፡ ወደ ፡
ማምለክ ፡ ይመለሱ ፡ ነበር ።
የዚያን ፡ ጊዜም ፡ መከራ ፡ የሚያጸኑባቸው ፡ አሕ ፳፯
ዛብን ፡ ያስነሣባቸው ፡ ነበር ፡ መከራ ፡ በጸኑብ
ቸው ፡ በሳዘኑዋቸውም ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ይጮሁ ፡ ነበር ፡ የሥልጣኑ ፡ ፍጥረት ፡
ስለሆኑ ፡ ይወዳቸዋልና ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ራርቶ ፡
ይቅር ፡ ይላቸው ፡ ነበር ።
ጽኑ ፡ በሆነ ፡ በእጃቸው ፡ ሥራና ፡ በሽንጓቸው ፡ ፳፰
ያለ ፡ ጣዖትን ፡ በማምለክ ፡ ያሳዝኑት ፡ ዘንድ ፡
በጠበቃቸው ፡ ጊዜ ፡ ዳግመኛም ፡ ወደ ፡ ኃጢ
አት ፡ ይመለሱ ፡ ነበር ።
እሱ ፡ ግን ፡ የሞዓብና ፡ የኢሎፍሊን ፡ የሶርያን ፡ ፳፱
የምድያምን ፡ የግብፅንም ፡ ሰዎች ፡ ያስነሣብ
ቸው ፡ ነበር ፤ ጠላቶቻቸውም ፡ ድል ፡ በነሷ
ቸው ፡ ጊዜ ፡ ይጮሁ ፡ ያለቅሱ ፡ ነበር ፡ መከራ ፡
ባፀኑባቸው ፡ ጊዜ ፡ ባስገበሩዋቸውም ፡ ጊዜ ፡
በገዟቸውም ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ በወደደ
በት ፡ ጊዜ ፡ ያድናቸው ፡ ዘንድ ፡ መሳፍንትን ፡
ያስነሣላቸው ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

በኢያሱም ፡ ጊዜ ፡ እነሳቸውን ፡ ያዳነበት ፡ ፩
ቀን ፡ አለ ።
በጌዴዎንም ፡ ጊዜ ፡ እነሳቸውን ፡ ያዳነበት ፡ ቀን ፡ ፪
አለ ።
በሶምሶንም ፡ ጊዜ ፡ በዲቦራና ፡ በባርቅ ፡ በዮዲ ፫
ትም ፡ ጊዜ ፡ እነሳቸውን ፡ ያዳነበት ፡ ቀን ፡ አለ ፡
በወንድና ፡ በሴትም ፡ ቢሆን ፡ አድሮ ፡ መከራ ፡
ከሚያጸኑባቸው ፡ ከጠላቶቻቸውም ፡ እጅ ፡ ያድ
ናቸው ፡ ዘንድ ፡ መሳፍንትን ፡ ያስነሣላቸው ፡
ነበር ።
መከራም ፡ ከሚያጸኑባቸው ፡ ሰዎች ፡ እግዚአ ፬
ብሔር ፡ እንደ ፡ ወደደ ፡ ያድናቸው ፡ ነበር ።
ባከናወነላቸውም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ፈጽሞ ፡ ደስ ፡ ፭
ይላቸው ፡ ነበር ፡ በምድራቸው ፡ ዘር ፡ በምድረ ፡
በዳ ፡ ያለ ፡ መንጋቸውን ፡ ሁሉና ፡ ከብታቸው
ንም ፡ በማብዛት ፡ ደስ ፡ ይላቸው ፡ ነበር ።
ተክላቸውንና ፡ ከብታቸውንም ፡ ይባርክላቸው ፡ ፮
ነበር ፡ በምድረ ፡ በዳና ፡ በቤት ፡ የያዙትንም ፡
ሁሉ ፡ ይባርክላቸው ፡ ነበር ፡ በዓይነ ፡ ምሕረት ፡
ያያቸዋልና ፡ ከብታቸውንም ፡ አያሳንስባቸ
ውም ፡ ነበርና ፡ የደጋግ ፡ ሰዎች ፡ ልጆች ፡ ናቸ
ውና ፡ ፈጽሞም ፡ ይወዳቸው ፡ ነበር ።
እነሳቸው ፡ ግን ፡ በሥራቸው ፡ ክፉ ፡ በሆኑ ፡ ፯
ጊዜ ፡ በጠላቶቻቸው ፡ እጅ ፡ ይጥላቸው ፡ ነበር ።
በጠፉቸውም ፡ ጊዜ ፡ በአምልኮ ፡ ይሹት ፡ ነበር ፡ ፰
ከኃጢአትም ፡ ተመልሰው ፡ በንስሐ ፡ ወደ ፡
እግዚአብሔር ፡ ይገሠግሡ ፡ ነበር ።
በፍጹም ፡ ልቡናቸውም ፡ በተመለሱ ፡ ጊዜ ፡ ፱
ኃጢአታቸውን ፡ ያስተሰርይላቸው ፡ ነበር ፡
ሥጋዊ ፡ ደማዊ ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ ያውቃቸዋልና ፡
የሚያስት ፡ የዚህ ፡ ዓለም ፡ አሳብ ፡ አለባቸውና ፡
አጋንንትም ፡ አሉባቸውና ፡ የቀደመ ፡ ኃጢአ

ቃቸውን ፡ አያስብባቸውም ፡ ነበር ።
፲ ያ ፡ መቃቢስ ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ በመመስገ
ኛው ፡ በታ ፡ በቤተ ፡ መቅደስ ፡ የሠራውን ፡
ይህን ፡ ሥራት ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ በንስሐ ፡ ተጋደለ ።
፲፩ ይኸንን ፡ ከየ ፡ ከሰማ ፡ በኋላ ፡ በኅ ፡ ሥራ ፡ መሥ
ራትን ፡ አላቃለለም ፡ እግዚአብሔር ፡ ይቅር ፡
በላቸው ፡ ጊዜ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ የሚሠ
ሩትን ፡ በጎውን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ መሥራት ፡ አላ
ቃለለም ፡ ከሕጉም ፡ ከተላለፉ ፡ በኋላ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ በመከራው ፡ በገረፋቸው ፡ ጊዜ ፡ ያለቅ
ሳሉ ፡ ይጮሁም ፡ ነበር ፡ ዳግማኛም ፡ ይቅር ፡
ይላቸው ፡ ነበር ፡ ሕጉንም ፡ ይጠብቋት ፡ ነበር ።
፲፪ መቃቢስም ፡ እንደዚሁ ፡ ሥራውን ፡ ያቃና ፡
ነበር ፡ ሕጉንም ፡ ይጠብቅ ፡ ነበር ፡ በእስራኤል ፡
ፈጣሪ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ትእዛዝም ፡ ፀንቶ ፡
ይኖር ፡ ነበር ።
፲፫ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ የሚመ
ኩብትን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ከሰማ ፡ በኋላ ፡ የእግዚ
አብሔርን ፡ ሕግ ፡ በመጠበቅ ፡ እንደነሳቸው ፡
ይመከ ፡ ነበር ።
፲፬ ወገኑን ፡ ልጆችንም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ትእዛ
ዝና ፡ በሕጉ ፡ ሁሉ ፡ ጸንተው ፡ ይኖሩ ፡ ዘንድ ፡
ይሠራራ ፡ ነበር ።
፲፭ እስራኤል ፡ የሚከለክሉትን ፡ ሥራት ፡ እሱም ፡
ይከለክል ፡ ነበር ፡ እስራኤልም ፡ የሚጠብቋትን ፡
ሕግ ፡ ሰምቶ ፡ ይጠብቅ ፡ ነበር ፡ ወገኑ ፡ ሌላ ፡ የሞ
ዓብ ፡ ሰው ፡ ሲሆን ፡ እስራኤል ፡ የሚከለክሉ
ትን ፡ ምግብ ፡ ይከለክል ፡ ነበር ።
፲፮ አሥራትም ፡ ያወጣ ፡ ነበር ፡ ከላሞቹና ፡ ከበጎቹ ፡
ከህዮቹም ፡ መጀመሪያ ፡ የተወለደውን ፡ የግዛ
ውንም ፡ ሁሉ ፡ ይሰጥ ፡ ነበር ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳ
ሌም ፡ ፊቱን ፡ መልሶ ፡ እስራኤል ፡ የሚሠዉ
ትን ፡ መሥዋዕት ፡ ይሠዋ ፡ ነበር ።
፲፯ የኀጢአትና ፡ የስለትን ፡ መሥዋዕት ፡ ድኅነት ፡
የሚደረግበት ፡ መሥዋዕትንና ፡ የፈቃድን ፡
መሥዋዕት ፡ የዘወትሩንም ፡ መሥዋዕት ፡ ይሠዋ ፡
ነበር ።
፲፰ ያገዘመራውንም ፡ መጀመሪያ ፡ ይሰጥ ፡ ነበር ፡
እስራኤል ፡ የሚያፈሱት ፡ ወይኑንም ፡ ፍልቅ ፡
አድርጎ ፡ ያፈስ ፡ ነበር ፡ ለሾመው ፡ ለካህኑም ፡
ይህነን ፡ ይሰጥ ፡ ነበር ፡ እስራኤልም ፡ የሚያደ
ርጉትን ፡ ሁሉ ፡ እንደዚሁ ፡ ያደርግ ፡ ነበር ፡
ዕጣኑንም ፡ ያጣፍጥ ፡ ነበር ።
፲፱ መቅረዝን ፡ ጋንን ፡ መንበርን ፡ ድንኳንን ፡ አራ
ቱን ፡ ኅብረ ፡ ቀለበትን ፡ ለቅድስተ ፡ ቅዱሳኑ ፡
መብራት ፡ የሚሆን ፡ የተከለሰ ፡ ዘይትንም ፡ እግ
ዚአብሔርን ፡ ባገለገሉት ፡ ጊዜ ፡ እስራኤል ፡
በቅድስተ ፡ ቅዱሳኑ ፡ የሚያደርጉት ፡ መጋረጃ
ንም ፡ አሠራ ።
፳ በሥራቱና ፡ በሕጉም ፡ ጸንተው ፡ በኖሩ ፡ ጊዜ ፡
እግዚአብሔርም ፡ ቸል ፡ ብሎ ፡ በጠላቶቻቸው ፡
እጅ ፡ ባልጣላቸው ፡ ጊዜ ፡ በጎ ፡ ሥራን ፡ እንደ
ሠሩ ፡ መቃቢስም ፡ እንደሳቸው ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡
ይሠራ ፡ ነበር ።

መምህር ፡ ይሆነው ፡ ዘንድ ፡ ከመረጣቸው ፡ ፈቃ ፳፩
ዱንም ፡ ከደረጉ ፡ ከእስራኤል ፡ ወገኖችም ፡
እንዳይለየው ፡ ሁልጊዜ ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡
ፈጣሪ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይለምን ፡ ነበር ።
በጽዮን ፡ ልጅን ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ ቤትን ፡ ፳፪
ይሰጠው ፡ ዘንድ ፡ በጽዮን ፡ ሰማያዊት ፡ ዘርዐ ፡
ምግባርን ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ሰማያዊት ፡ ቤተ ፡
ነፍስን ፡ ይሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ በነቢዩ ፡ እንደበት ፡
ከተናገረው ፡ ከጥፋትም ፡ ያድነው ፡ ዘንድ ፡
አገዛ ፡ ንስሐ ፡ ገብቶ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
ባለቀሰው ፡ ልቅሶ ፡ ሁሉ ፡ ንስሐውን ፡ ይቀበ
ለው ፡ ዘንድ ።
በዚህም ፡ ዓለም ፡ ልጅን ፡ እንዳያጠፋበት ፡ ፳፫
በመውጣቱና ፡ በመግቢቱም ፡ ይጠብቀው ፡
ዘንድ ፡ ዳግመኛ ፡ ይለምን ፡ ነበር ።
አለቃቸው ፡ በቀናች ፡ ሥራ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራልና ፡ ፳፬
በመቃቢስ ፡ ሥልጣን ፡ በታች ፡ ካሉ ፡ ከሞዓብ ፡
አሕዛብ ፡ ወገኖች ፡ ያምኑ ፡ ዘንድ ፡ ደስ ፡ አላቸው ፡
ፍርዱንም ፡ ይመለከቱ ፡ ነበር ፡ ፈቃዱንም ፡ ይፈ
ጽሙ ፡ ነበር ፡ ያገራቸውን ፡ ቋንቋ ፡ ያገራቸው
ንም ፡ ፍርድ ፡ ይንቁ ፡ ነበር ፡ የመቃቢስ ፡ ሥራ ፡
እንዲበልጥ ፡ እንዲቀና ፡ ያስተውሉ ፡ ነበር ።
እነሱም ፡ መጥተው ፡ የመቃቢስን ፡ የቸርነቱንና ፡ ፳፭
የውነቱን ፡ ፍርድ ፡ ይሰሙ ፡ ነበር ።
ብዙ ፡ ገንዘብ ፡ ነበረው ፡ ሴቶች ፡ በሮችና ፡ ወን ፳፮
ዶች ፡ በሮች ፡ ግመሎችና ፡ አህዮችም ፡ ነበሩት ፡
ጥሩር ፡ የሚለብሱ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ፈረሰችም ፡
ነበሩት ፡ አማሌቃውያንና ፡ ኢሎፍላውያንን ፡
የሶርያንም ፡ ሰዎች ፡ ፈጽሞ ፡ ድል ፡ ይነሳቸው ፡
ነበር ፡ ቀድሞ ፡ ጣዖት ፡ ሲያመልክ ፡ ግን ፡ ድል ፡
ሲነሱት ፡ ኖረ ።
እሱ ፡ ድል ፡ ነሣ ፡ እንጂ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፳፯
ካመለከ ፡ ወዲህ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ሰልፍ ፡ ሲሔድ ፡
እሱን ፡ ድል ፡ የነሣው ፡ የለም ።
እነሳቸው ፡ ግን ፡ ይወጉት ፡ ዘንድ ፡ በጣዖታ ፳፰
ቸው ፡ ኃይል ፡ ይመጡ ፡ ነበር ፡ የጣዖቶቻቸ
ውንም ፡ ስም ፡ ጠርተው ፡ ይረግሙት ፡ ነበር ፡
እምነቱን ፡ በፈጣሪው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡
አድርጓልና ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ድል ፡ የሚነሣው ፡
አልነበረም ።
እንዲህ ፡ ሲያደርግ ፡ ጠላቶቹንም ፡ ድል ፡ ሲነሣ ፡ ፳፱
አሕዛብንም ፡ በሥልጣኑ ፡ ሲገዛ ፡ ኖረ ።
የተበደሉ ፡ ሰዎች ፡ ጠላታቸውን ፡ ተበቅሎ ፡ ፴
ያጠፋላቸው ፡ ነበር ፡ እናት ፡ አባቱ ፡ ለሞቱበት ፡
ልጅ ፡ እውነት ፡ ይፈርድ ፡ ነበር ።
ባልቴቶችንም ፡ በችጋራቸው ፡ ጊዜ ፡ ይቀበላ ፴፩
ቸው ፡ ነበር ፡ የተራቡትንም ፡ ከምግቡ ፡ ሰጥቶ ፡
ያጠግባቸው ፡ ነበር ፡ የተራቆቱትንም ፡ ከልብሱ ፡
ያለብሳቸው ፡ ነበር ።
በጁም ፡ ሥራ ፡ ደስ ፡ ይለው ፡ ነበር ፡ ሳይነፍግ ፡ ፴፪
ከለውም ፡ ገንዘብ ፡ ይሰጥ ፡ ነበር ፡ ለቤተ ፡ መቅ
ደስም ፡ አሥራትን ፡ ይሰጥ ፡ ነበር ፡ መቃቢስ ፡
ይኸንን ፡ ሲያደርግ ፡ በተድላ ፡ በደስታ ፡ ኖሮ ፡
ሞተ ።

ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ ታናናሽ ፡ የሆኑ ፡ ልጆቹንም ፡ ትቶ ፡ ሞተ ፡
አባታቸውም ፡ እንዳስተማራቸው ፡ አደጉ ፡ የቤ
ታቸውንም ፡ ሥራት ፡ ጠበቁ ፡ ወገናቸውን ፡
ሁሉ ፡ ይጠብቁ ፡ ነበር ፡ ድኃን ፡ ባልቴቶችንና ፡
እናት ፡ አባቱ ፡ የሞቱበት ፡ ልጅንም ፡ አያስጮ
ሁም ፡ ነበር ።
፪ እግዚአብሔርን ፡ ይፈሩት ፡ ነበር ፡ ገንዘባቸው
ንም ፡ ለድኃ ፡ ይመጸውቱ ፡ ነበር ፡ አባታቸ
ውም ፡ አደራ ፡ ያላቸውን ፡ ሁሉ ፡ ይጠብቁ ፡
ነበር ፡ እናት ፡ አባቱ ፡ የሞቱበትን ፡ ልጅንና ፡
ባልቴቶችንም ፡ በችጋራቸው ፡ ጊዜ ፡ ያረጋጓ
ቸው ፡ ነበር ፡ እናትና ፡ አባትም ፡ ይሆኗቸው ፡ ነበር ፡
ከሚበድሏቸው ፡ ሰዎች ፡ እጅ ፡ ያስጥሏቸው ፡
ከገኛቸው ፡ ሁከትና ፡ ኀዘንም ፡ ሁሉ ፡ ያረጋጓ
ቸው ፡ ነበር ።
፫ እንዲህ ፡ እያደረጉ ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ኖሩ ።
፬ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ የከለዳውያን ፡ ንጉሥ ፡ ጺሩጻይ
ዳን ፡ መጣ ፡ አገራቸውን ፡ ሁሉ ፡ አጠፋ ፡ የመ
ቃቢስንም ፡ ልጆች ፡ ማረካቸው ፡ መንደራቸው
ንም ፡ ሁሉ ፡ አጠፋ ።
፭ ገንዘባቸውንም ፡ ሁሉ ፡ ዘረፈ ፡ በክፉ ፡ ሥራ ፡
ሁሉና ፡ በኃጢአት ፡ በዝሙት ፡ በስድብና ፡ በስ
ስት ፡ ፈጣሪያቸውንም ፡ ባለማሰብ ፡ ጸንተው ፡
ይኖራሉ ፡ እንጂ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ሕግና ፡ በት
እዛዙ ፡ ጸንተው ፡ የማይኖሩ ፡ ጣዖት ፡ የሚ
ያመልኩ ፡ ሰዎች ፡ እነሳቸውንም ፡ ይዘው ፡
ወደ ፡ አገራቸው ፡ ወሰዷቸው ።
፮ አውሬ ፡ የነከሰውንና ፡ ደሙን ፡ በክቱን ፡ አበላ ፡
መትተው ፡ የጣሉትን ፡ እግዚአብሔር ፡ የማይ
ወደውን ፡ ሁሉ ፡ ይበላሉ ፡ እንጂ ፡ በኦሪት ፡ ከተ
ጻፈው ፡ ከውነተኛ ፡ ተእዛዝ ፡ ሁሉ ፡ ሥራት ፡
የላቸውም ።
፯ ከናታቸው ፡ ማኅፀን ፡ ያወጣቸው ፡ በሚገባም ፡
የመገባቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፈጣሪያቸው ፡
መድኃኒታቸው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አያውቁትም ።
፰ አክስታቸውንና ፡ ያባታቸውን ፡ ሚስት ፡ የእን
ጀራ ፡ እናታቸውን ፡ አግብተው ፡ ወደ ፡ ቅሚ
ያና ፡ ወደ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ወደ ፡ ኃጢአትና ፡ ወደ ፡
ዝሙትም ፡ ይሄዳሉ ፡ እንጂ ፡ በፍርድ ፡ ጊዜ ፡
ሥራት ፡ የላቸውም ፡ ክፉ ፡ ሥራንም ፡ ሁሉ ፡
ይሠራሉ ፡ አክስቶቻቸውንምና ፡ እኅቶቻቸው
ንም ፡ ያገባሉ ፡ ሕግም ፡ የላቸው ።
፱ መንገዳቸውም ፡ ሁሉ ፡ ጨለማና ፡ ድጥ ፡ ነው ፡
ሥራቸውም ፡ ኃጢአትና ፡ ዝሙት ፡ ነው ።
፲ እነዚያ ፡ የመቃቢስ ፡ ልጆች ፡ ግን ፡ በሥራታ
ቸው ፡ ሁሉ ፡ ይጠብቁ ፡ ነበር ፡ አበላ ፡ የመታው
ንና ፡ ሙቶ ፡ ያደረውን ፡ አይበሉም ፡ ነበር ፡
በዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ ያልተጻፈ ፡ ኃጢአተኞች ፡
ተጠራጣሪዎችና ፡ ወንጀለኞች ፡ ቅሚያንና ፡
ኃጢአትን ፡ ፈጽመው ፡ የተመሉ ፡ የሚሆኑ ፡
ከዳተኞች ፡ የአረማውያን ፡ ልጆች ፡ የሚሠሩት ፡
ብዙ ፡ የሆነ ፡ ሥራቸው ፡ ክፉ ፡ ነውና ፡ የከለዳ
ውያን ፡ ልጆች ፡ የሚሠሩትን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡
አይሠሩም ፡ ነበር ።
ፈጣሪያቸው ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚወደው ፡ ፲፩
ሥራ ፡ ሁሉ ፡ በነሳቸው ፡ ዘንድ ፡ የለም ።
ዳግመኛም ፡ ብኤል ፡ ፌጎር ፡ የሚባል ፡ ጣዖትን ፡ ፲፪
ያመልኩ ፡ ነበር ፡ ደንቆሮ ፡ ዲዳ ፡ ሲሆን ፡ እንደ ፡
ፈጣሪያቸው ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይታመ
ኑት ፡ ነበር ። የሰው ፡ እጅ ፡ የሠራው ፡ ጣዖት ፡
ነውና ፡ ብርና ፡ ወርቅን ፡ የሚሠራ ፡ አንጥረኛ ፡
የሠራው ፡ ትንፋሽና ፡ እውቀት ፡ የሌለው ፡
የሰው ፡ እጅ ፡ ሥራ ፡ ነውና ፡ የሚያየውም ፡
የሚሰማውም ፡ አልነበረውም ።
አይበላም ፡ አይጠጣም ። ፲፫
አይገድልም ፡ አያድንም ። ፲፬
አይተክልም ፡ አይነቅልም ። ፲፭
ጠላቱን ፡ አይገሎዳም ፡ ወዳጁንም ፡ አይጠቅምም ። ፲፮
አያደኽይም ፡ አያከብርም ። ፲፯
ሰነፎች ፡ የሆኑ ፡ የከለዳውያንን ፡ ሰዎች ፡ ለማ ፲፰
ሳት ፡ ዕንቅፋትን ፡ ይሆናል ፡ እንጂ ፡ አይቀሥ
ፍም ፡ ይቅር ፡ አይልም ።

ምዕራፍ ፡ ፱ ።

የእግዚአብሔር ፡ ጠላት ፡ ትቢተኛ ፡ የሆነ ፡ ጺሩ ፩
ጻይዳን ፡ ለጣዖታቱ ፡ የሚጋርዱና ፡ የሐሰት ፡
ካህናቶችን ፡ ሾመ ።
መሥዋዕት ፡ ይሠዋላቸው ፡ ነበር ፡ ወይኑንም ፡ ፪
ያፈስላቸው ፡ ነበር ።
እነሳቸውም ፡ የሚበሉ ፡ የሚጠጡ ፡ ይመስለው ፡ ፫
ነበር ።
እየነጋም ፡ በጎችንና ፡ ላሞችን ፡ ፍየሎችንና ፡ ፬
ጊደሮችንም ፡ ይሰጣቸው ፡ ነበር ፡ ጧትና ፡
ማታም ፡ መሥዋዕት ፡ ይሠዋ ፡ ነበር ፡ ከዚያች ፡
ከረከሰች ፡ መሥዋዕትም ፡ ይበላ ፡ ነበር ።
ለጣዖታቱ ፡ ይሠዉ ፡ ዘንድ ፡ ዳግመኛም ፡ ሌሎች ፡ ፭
ሰዎችን ፡ ያውኳቸው ፡ ግድ ፡ ይሏቸው ፡ ነበር ፡
እንጂ ፡ እነሳቸው ፡ ብቻ ፡ የሚያደርጉት ፡ አል
ነበረም ።
የመቃቢስን ፡ ልጆች ፡ ያማሩ ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ ፮
ፈጣሪያቸው ፡ እግዚአብሔርንም ፡ እንዲያመል
ኩት ፡ ባዩዋቸው ፡ ጊዜ ፡ መሥዋዕት ፡ እንዲ
ሠዉ ፡ ከዚያች ፡ ከተጠላች ፡ መሥዋዕትም ፡ እን
ዲበሉ ፡ የጣዖታቱ ፡ ካህናት ፡ ያስቷቸው ፡ ዘንድ ፡
ወደዱ ፡ እለዚህ ፡ የከበሩ ፡ የመቃቢስ ፡ ልጆች ፡
ግን ፡ እምቢ ፡ አሏቸው ።
ያባታቸውን ፡ ትእዛዝ ፡ ይጠብቃሉና ፡ በጎ ፡ ፯
ሥራንም ፡ በመሥራት ፡ ጸንተዋልና ፡ እግዚአ
ብሔርንም ፡ ፈጽመው ፡ ይፈሩታልና ፡ እነሳ
ቸውን ፡ እሺ ፡ ማሰኘት ፡ ተሳናቸው ።
ባሠሯቸው ፡ በሰደቧቸው ፡ በቀሟቸውም ፡ ጊዜ ። ፰
ለጣዖቶቹ ፡ መሥዋዕቱንና ፡ መስገድን ፡ እምቢ ፡ ፱
እንዳሉ ፡ ለንጉሡ ፡ ለጺሩጻይዳን ፡ ነገሩት ።
ስለዚህም ፡ ነገር ፡ ንጉሡ ፡ ተቈጣ ፡ አዘነ ፡ ያመ ፲
ጧቸውም ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፡ አምጥተውም ፡
በፊቱ ፡ አቆማቸው ፡ ለጣዖቱ ፡ ንጉሡም ፡ ለጣ

ያዩቸ ፡ መሥዋዕት ፡ ሠዉ ፡ አላቸው ።
፲፩ እነሳቸውም ፡ ተናገሩ ፡ በዚህም ፡ ነገር ፡ እንመለ
ስልህም ፡ ለረከሱ ፡ ለጣዖቶችህም ፡ መሥዋዕት ፡
እንሠዋም ፡ አሉት ።
፲፪ በበዙ ፡ ሥራ ፡ አስፈሩቸው ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ አምነው ፡ ልቡናቸውን ፡ አስጨክነዋልና ፡
ነገር ፡ ግን ፡ አልቻላቸውም ።
፲፫ እሳት ፡ አንድዶ ፡ በእሳት ፡ ላይ ፡ ጣላቸው ፡ እነ
ሳቸውም ፡ ሰውነታቸውን ፡ ለእግዚአብሔር ፡
ሰጡ ።
፲፬ ከሞቱ ፡ በኋላ ፡ ተነሥተው ፡ ሰይፋቸውን ፡
መዘው ፡ በጌትነቱ ፡ ዙፋን ፡ ተኝቶ ፡ ሳለ ፡ ሌሊት ፡
ታዩት ፡ እሱም ፡ ፈጽሞ ፡ ፈራ ።
፲፭ ጌቶቼ ፡ እሺ ፡ በሉኝ ፡ ምን ፡ ላድርግላችሁ ፡ ያዘ
ዛችሁኝን ፡ ሁሉ ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ ሰውነቴን ፡
በሞት ፡ አትውሰዷት ፡ አላቸው ፡ ፈጽመውም ፡
አስፈሩት ።
፲፮ እግዚአብሔር ፡ ፈጣሪህ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አስብ ፡
እያሉ ፡ የሚገባውን ፡ ሁሉ ፡ ነገሩት ፡ ከዚህም ፡
ከምትታበይበት ፡ መንግሥትህ ፡ ሽሮ ፡ ከበትህ ፡
ከዲያብሎስ ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ ገሃነመ ፡ እሳት ፡ የሚ
ያወርድህ ፡ እግዚአብሔር ፡ አለ ፡ አንተን ፡ የበ
ደልንህ ፡ በደል ፡ ሳይኖር ፡ ፈጣሪያችን ፡ እግዚ
አብሔርን ፡ ስናመልከው ፡ እግዚአብሔርነቱ
ንም ፡ በመፍራት ፡ ስንሰግድለት ፡ በእሳት ፡ እን
ዳቃጠልኸን ፡ በዚያም ፡ ፍዳህን ፡ ሁሉ ፡ ትጨ
ርሳለህ ።
፲፯ እሱ ፡ ሁሉን ፡ የፈጠረ ፡ነውና ፡ ምድርና ፡ ሰማ
ይን ፡ ባሕርንም ፡ በውስጧ ፡ ያለውንም ፡ ሁሉ ።
፲፰ ጨረቃና ፡ ፀሐይንም ፡ ከዋክብትንም ፡ የፈጠረ ፡
ነውና ፡ ፍጥረቱንም ፡ ሁሉ ፡ የፈጠረ ፡ እሱ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ነውና ።
፲፱ በምድርና ፡ በሰማይ ፡ ያለሱ ፡ ሌላ ፡ ፈጣሪ ፡ የለ
ምና ፡ ሁሉን ፡ የሚችል ፡ እሱ ፡ ነውና ፡ የሚሳ
ነውም ፡ የለምና ። የሚገድል ፡ የሚያድን ፡ በመ
ከራ ፡ የሚገርፍ ፡ ይቅር ፡ የሚል ፡ እሱ ፡ ነውና ፡
እግዚአብሔርን ፡ በመፍራት ፡ ስንሰግድለት ፡
በእሳት ፡ እንዳቃጠልኸን ፡ በዚያ ፡ ፍዳህን ፡ ትጨ
ርሳለህ ፡ አሉት ።
፳ ምድርና ፡ ሰማይን ፡ የሚገዛ ፡ እሱ ፡ ነውና ፡ ከሥ
ልጣኑ ፡ የሚያመልጥ ፡ የለም ።
፳፩ ወንጀለኛ ፡ ከምትሆን ፡ ካንተ ፡ አባትህ ፡ ሰይ
ጣን ፡ ልቡናቸውን ፡ ከሠወራቸው ፡ እንዳንተ ፡
ካሉ ፡ ከወንጀለኞች ፡ በቀር ፡ እሱ ፡ ከፈጠረው ፡
ፍጥረት ፡ ከትእዛዙ ፡ የወጣ ፡ የለም ፡ አንተና ፡
እነዚያ ፡ ካህናቶችህም ፡ ጣዖታቶችህም ፡ እስከ ፡
ዘላለም ፡ ድረስ ፡ መውጫ ፡ ወደ ፡ ሌለበት ፡ ወደ ፡
ገሃነም ፡ ባንድነት ፡ ትወርዳላችሁ ።
፳፪ በኛ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ፡ ይኸን ፡ ክፉ ፡
ሥራ ፡ ያስተማረህ ፡ መምርህ ፡ ሰይጣን ፡ ነው ፡
እንጂ ፡ ይኸን ፡ የምታደርግ ፡ አንተ ፡ብቻ ፡ አይ
ደለህምና ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡ ባንድነት ፡ ትወርዳላ
ችሁ ።
፳፫ ራስህን ፡ እንደ ፡ ፈጣሪህ ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡
ታደርጋለህ ፡ እንጂ ፡ የፈጠረህ ፡ እግዚአብሔ
ርን ፡ አላወቅኸውምና ።
እግዚአብሔር ፡ እስኪያገሰቅልህ ፡ ድረስ ፡ ፳፬
በጣዖትህና ፡ በጅህም ፡ ሥራ ፡ ትታበያለህ ፡
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ስለ ፡ ሠራኸው ፡ ኃጢአትህ ፡
በደልህ ፡ ሁሉ ፡ ይፈርድብሃል ።

ምዕራፍ ፡ ፯ ።

የፈጠራችሁ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለማታውቁ ፡ ፩
እንዳንተ ፡ ላሉ ፡ ለጣዖቶችህና ፡ ላንተ ፡ ወዮላ
ችሁ ፡ በሲኦል ፡ ጭንቅም ፡ ተይዛችሁ ፡ በዘና
ችሁ ፡ ጊዜ ፡ በማይረባ ፡ ጸጸትን ፡ ትጸጸቱ ፡
ዘንድ ፡ አላችሁና ፡ ቃሉንና ፡ ሕጉንም ፡ ለማት
ጠብቁ ፡ ለናንተ ፡ ወዮልህ ።
ትንፋሽና ፡ ነፍስ ፡ ለሌላቸው ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ፪
ያደረገባቸውን ፡ ተበቅለው ፡ ለማያጠፉ ፡ በጎ ፡
ነገር ፡ ላደረገላቸውም ፡ በጎ ፡ ነገርን ፡ ለማያደ
ርጉ ፡ ለጣዖቶችህ ፡ እንደ ፡ ፈጣሪያችሁ ፡ እንደ ፡
እግዚአብሔር ፡ ለምትሠዋላቸው ፡ ለካህናቶች
ህና ፡ ላንተ ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ድረስ ፡ ከዚ ፡
መውጫ ፡ የላችሁም ።
ለናንተ ፡ የሚታዘዙዋችሁ ፡ አጋንንትና ፡ ጣዖ ፫
ቶቻችሁን ፡ የሚያገለግሉ ፡ ካህናቱንም ፡ ወደ ፡
ገሃነመ ፡ እሳት ፡ ያወርዳችሁ ፡ ዘንድ ፡ እንዳንተ ፡
ያሉ ፡ የሰነፎችን ፡ ልቡና ፡ ለማሳት ፡ አድሮባ
ቸው ፡ ሰይጣን ፡ የሚኖርባቸው ፡ የሰው ፡ እጅ ፡
ሥራ ፡ ናቸውና ፡ ለምትሠውላቸው ፡ ለናንተ ፡
ወዮላችሁ ።
የሚረባችሁ ፡ እንደሌለ ፡ አታውቁምና ፡ ትበድ ፬
ላላችሁ ፡ ትስታላችሁ ።
እነሳቸው ፡ ያላንዷት ፡ ሞት ፡ ዳግመኛ ፡ ከኑኔ ፡ ፭
የለባቸውምና ፡ ከናንተስ ፡ ምግብ ፡ ሊሆኗችሁ ፡
እግዚአብሔር ፡ የፈጠራቸው ፡ እንስሳት ፡ ውሾ
ችና ፡ አውሬዎችም ፡ ይሻላሉ ።
እናንተ ፡ ግን ፡ ሞታችሁ ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ድረስ ፡ ፮
መውጫ ፡ በሌለበት ፡ በገሃነም ፡ እሳት ፡ ፍዳ ፡
ትቀበላላችሁና ፡ እንስሳት ፡ ይሻላሉ ።
ይኸንን ፡ ተናግረው ፡ ሄዱ ፡ ከሱም ፡ ተሠወሩ ። ፯
ያ ፡ ጺሩጻይዳን ፡ ግን ፡ በዕኑ ፡ ፍርሃት ፡ ተይዞ ፡ ፰
ሲንቀጠቀጥ ፡ አደረ ፡ እስኪነጋም ፡ ድረስ ፡ ፍር
ሃት ፡ አልተወውም ።
ይቀብሩቸው ፡ ዘንድ ፡ ወዷልና ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ፱
የጻድቃንን ፡ ሬሳ ፡ ወደ ፡ ጣለበት ፡ በታ ፡ ሂዶ ፡
ሬሳቸውን ፡ እንዳይነካ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሠውሯ
ቸዋልና ፡ ነገር ፡ ግን ፡ አጣቸው ።

ምዕራፍ ፡ ፰ ።

በልቡና ፡ ተንክልና ፡ በትዕቢትም ፡ ፀንቶ ፡ ኖረ ። ፩
በመንግሥቱም ፡ ዳንኤል ፡ እንዳየው ፡ ብረት ፡ ፪
ዕኑ ፡ ተብዒልና ፡ በዙሪያው ፡ ያሉ ፡ የአሕዛብ ፡
አገሮችን ፡ ዞረ ።
በክፋትና ፡ በስንፍናው ፡ ሁሉ ፡ ሰውንም ፡ በማ ፫
ወክ ፡ ፀንቶ ፡ ይኖራል ።

፬፣ ቀድሞም ፡ የተናገርነውን ፡ ፊጽሞ ፡ ያጠፋል ፡
የሰውንም ፡ ገንዘብ ፡ ይበላል ።
፭፣ ክፃደ ፡ ልቡናውን ፡ እንዳፀና ፡ እንደ ፡ አባቱ ፡
እንደ ፡ ዲያብሎስ ፡ ለክፋት ፡ የተጋ ፡ ነውና ፡
የቀረውንም ፡ በሠራዊቱ ፡ ያጠፋል ።
፮፣ ዘመኔ ፡ እንደ ፡ ሰማይ ፡ ዘመን ፡ ሆነ ፡ ይላል ፡
እንጂ ፡ ፈጣሪው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እግዚአብሔ
ርን ፡ አያውቀውም ።
፯፣ በልቡናውም ፡ ፀሐይ ፡ ከሱ ፡ እንዲገኝ ፡ ያስ
ባል ።
፰፣ በኃይል ፡ ይነሣል ፡ በነገደ ፡ ዛብሎን ፡ ዕጣ ፡
ሰፍሮ ፡ በመቄዶንያ ፡ ሰልፍ ፡ ይጀመራል ፡ ከሰ
ማርያም ፡ ምግቡን ፡ ይቀበላል ፡ ከሰማርያም ፡
እጅ ፡ መንሻን ፡ ይሰጡታል ።
፱፣ በዘላኖች ፡ አውራጃ ፡ ይሰፍራል ፡ እስከ ፡ ሲዶ
ናም ፡ ይደርሳል ፡ በአክይያም ፡ ግብር ፡ ይጥላል ፡
እስከ ፡ ፋሳሹ ፡ ባሕርም ፡ ድረስ ፡ ክፃደ ፡ ልቡ
ናውን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደርጋል ፡ ተመልሶም ፡
እስከ ፡ ሕንደኬ ፡ ባሕር ፡ ድረስ ፡ መልክተኞችን ፡
ይልካል ።
፲፣ እንደዚሁም ፡ ክፃደ ፡ ልቡናውን ፡ እስከ ፡ ሰማይ ፡
ድረስ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደርጋል ።
፲፩፣ በመታበይና ፡ በክፋት ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፡
እንጂ ፡ ራሱን ፡ ማዋረድ ፡ የለውም ።
፲፪፣ ኅዳናውም ፡ ወደ ፡ ጨለማና ፡ ወደ ፡ ድጥ ፡ ወደ ፡
ወንጀልና ፡ ወደ ፡ መታበይም ፡ ደም ፡ ወደ ፡
ማፍሰስና ፡ ወደ ፡ መከራም ፡ ነው ።
፲፫፣ ሥራውም ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚጠላው ፡
ነው ፡ የቅሚያና ፡ የክፋት ፡ የኃጢአት ፡ መም
ህር ፡ ዲያብሎስ ፡ እንዳስተማረው ፡ ያደርጋል ፡
እናቱና ፡ አባቱ ፡ የሞቱበትን ፡ ልጅ ፡ ያስጨ
ንቃል ፡ ለድኃም ፡ አይራራም ።
፲፬፣ የአሕዛብንም ፡ ነገሥታት ፡ በሥልጣኑ ፡ ድል ፡
ነሥቶ ፡ አጠፋቸው ።
፲፭፣ የጠላቶች ፡ አለቆችንም ፡ ገዛ ፡ ብዙ ፡ አሕዛብ
ንም ፡ ገዛ ፡ እንደ ፡ ወደደም ፡ አስገበራቸው ።
፲፮፣ ቢያጠፋም ፡ አልተወም ፡ ከተርሴስ ፡ ባሕር ፡
ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ኢያሪኮ ፡ ባሕር ፡ ድረስ ፡ ያልነ
ጠቀውም ፡ ሰው ፡ የለም ።
፲፯፣ ለጣዖት ፡ ይሰግድ ፡ ነበር ፡ ሙቶ ፡ ያደረውን ፡
ደሙን ፡ ሰይፍ ፡ ንሮ ፡ የቆረጠውን ፡ ለጣዖቶ
ችም ፡ የተሠዋውን ፡ ይበላ ፡ ነበር ፡ ሥራው ፡
ሁሉ ፡ ያለ ፡ ፍርድ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ፍርድ ፡ የለ
ውም ፡ ከሥልጣኑ ፡ በታች ፡ ያሉ ፡ አሕዛብን ፡
የሚያስደነግጥ ፡ ሁኗልና ፡ እንደ ፡ ወደደ ፡ ግብ
ርን ፡ ያስገብራቸው ፡ ነበር ።
፲፰፣ በፊቱ ፡ የወደደውን ፡ ሁሉ ፡ ያደርጋልና ፡ በፊቱ ፡
እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ የለም ፡ በፈጠረው ፡
በእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡ በተንኮል ፡ ይኖራል ።
፲፱፣ እንደ ፡ ፈጣሪው ፡ አላደረገውም ፡ ተቈጥቶም ፡
በያዘው ፡ ጊዜ ፡ በበልንጀራው ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ነገ
ርን ፡ እንዳደረገ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ፍዳውን ፡
ይከፍለዋል ።
፳፣ እግዚአብሔር ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ስም ፡ አጠራሩ
ቸውን ፡ አጠፋ ፡ ዘንድ ፡ በትእዛዜ ፡ የማይኖሩ ፡
ኃጢአተኞች ፡ ሰዎችን ፡ እኔ ፡ ተበቅዬ ፡ አጠፋ
ቸዋለሁ ፡ ብሏልና ፡ ከሱ ፡ አስቀድሞ ፡ የነበሩ ፡
ሰዎችን ፡ እንዳጠፋቸው ፡ በሚያጠፋበት ፡ ጊዜ ፡
ተበቅሎ ፡ ያጠፋዋል ።
ክፉ ፡ ሰዎችም ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ እንዳደረጉ ፡ ፍዳ ፳፩፣
ቸውን ፡ ይቀበላሉ ።
በጎ ፡ ሥራ ፡ የሚሠሩ ፡ ሰዎችን ፡ ግን ፡ ከእግዚ ፳፪፣
አብሔር ፡ ታዛ ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ ትከተላቸዋለች ።
ኢያሱ ፡ አምስቱ ፡ የከነዓን ፡ ነገሥታትን ፡ በን ፳፫፣
ዲት ፡ ቀን ፡ በዋሻ ፡ እንዳጠፋቸው ፡ ሠራዊቶ
ቻቸውንም ፡ ያጠፋቸው ፡ ዘንድ ፡ በጸሎቱ ፡ ፀሐ
ይን ፡ በገባዖን ፡ እንዳቆመ ፡ የኤዌዎንና ፡ የከና
ኔዎንን ፡ የፌርዜዎንና ፡ የኬጤዎንን ፡ የኢ
ያቡሴዎንንም ፡ ሠራዊት ፡ እስኪያጠፋቸው ፡
ድረስ ፡ ፀሐይ ፡ በሰማይ ፡ መካከል ፡ ቆሟልና ፡
በንድ ፡ ጊዜ ፡ ሁለት ፡ እልፍ ፡ ያህል ፡ ሰውም ፡
እንደ ፡ ገደለ ፡ እነሳቸውንም ፡ እንደ ፡ ገደላቸው ፡
እግር ፡ ከንገትም ፡ አድርጎ ፡ እንዳሠራቸው ፡
በዋሻም ፡ በጦር ፡ እንደ ፡ ገደላቸው ፡ ደንጊያም ፡
እንደ ፡ ገጠመባቸው ።
በክፉ ፡ ሥራቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚያሳ ፳፬፣
ዝኑት ፡ ሰዎችን ፡ ሁሉ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ መከራ ፡
ያገኛቸዋል ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

እግዚአብሔር ፡ ያይደለህ ፡ ደካማ ፡ ሰው ፡ ሆይ ፡ ፩፣
ለምን ፡ ትኮራለህ ፡ ዛሬ ፡ ሰው ፡ ሆነህ ፡ የምት
ታይ ፡ አንተ ፡ ነገ ፡ መሬት ፡ አመድ ፡ ነህ ፡ በመ
ቃብርም ፡ ፈጽመህ ፡ ትል ፡ ትሆናለህ ።
ያንተ ፡ መምህር ፡ አባታችን ፡ አዳምን ፡ ስላ ፪፣
ሳተ ፡ የሰውን ፡ ሁሉ ፡ ኃጢአት ፡ ፍዳ ፡ ወደ
ራሱ ፡ የሚመልስ ፡ ዲያብሎስ ፡ ነውና ፡ ዳግመ
ኛም ፡ ሲኦል ፡ ታገኝሃለች ፡ ያንተንም ፡ ኃጢ
አት ፡ የሚሠሩ ፡ ሰዎችን ፡ ታገኛቸዋለች ።
ክፃደ ፡ ልቡናውን ፡ በማጽናትና ፡ ራሱን ፡ በማ ፫፣
ኩራት ፡ ፈጣሪው ፡ ለፈጠረው ፡ ለአዳም ፡ መስ
ገድን ፡ እምቢ ፡ እንዳለ ።
አንተም ፡ መምርህ ፡ ዲያብሎስ ፡ እንዳደረገ ፡ ፬፣
ለፈጣሪህ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መስገድ ፡ እምቢ ፡
ብለሃልና ።
ፈጣሪያቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ በአምልኮ ፡ የማ ፭፣
ያውቁት ፡ የቀደሙ ፡ አባቶችህ ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡
እንዲሄዱ ፡ አንተም ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡ ትሄዳለህ ።
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ስለ ፡ ሠሩት ፡ ስለ ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፮፣
ቸው ፡ ተበቅሎ ፡ እንዳጠፋቸው ፡ ወደ ፡ ገሃነ
ምም ፡ እንደ ፡ ወረዱ ።
አንተም ፡ እንደነሳቸው ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡ ትወር ፯፣
ዳለህ ።
ቀጣውን ፡ አነሳስተሃልና ፡ በምስቱም ፡ መንግ ፰፣
ሥታት ፡ ላይ ፡ ሥልጣን ፡ የሰጠህ ፡ እግዚአብሔ
ርንም ፡ ማምለክ ፡ ቸል ፡ ብለሃልና ፡ ከእግዚአብ
ሔር ፡ ሥልጣን ፡ የምታመልጥ ፡ ይመስልሃልን ።
ፈቃዱን ፡ ታደርግ ፡ እንደሁ ፡ አታደርግም ፡ ፱፣

እንደሁ ፡ መረመረሀ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡
ብትሠራ ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ሥራህን ፡ ሁሉ ፡
ያከናውንልሃል ፡ በጅህም ፡ የያዝኸውን ፡ ሥራ ፡
ሁሉ ፡ ያከናውንልሃል ፡ ይባርክልሃል ፡ ጥንተ ፡
ጠላቶችህንና ፡ የለት ፡ ጠላቶችህንም ፡ ያስገዛ
ልሃል ።
፲፤ በመግባትህና ፡ በመውጣትህ ፡ ከበሕርይህ ፡ በተ
ወለደ ፡ ልጅህም ፡ በመንጋዎችህና ፡ በድልበ
ችህም ፡ እጅህንም ፡ በዋርክበት ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡
በልብህም ፡ በሰብከው ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ ይልሃል ፡
እንዲሀ ፡ ቃደርግ ፡ ዘንድ ፡ ትሠራ ፡ ትተክል ፡
ታፈርስም ፡ ዘንድ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡
ሥልጣን ፡ ተሰጥቶሃልና ፡ ሁሉ ፡ ይታዘዝልሃል ።
፲፩፤ ነገር ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ባትሰማ ፡
በሕጉም ፡ ጸንተህ ፡ ባትኖር ፡ የእግዚአብሔር ፡
ፍርዱ ፡ እውነት ፡ ነውና ፡ ከንተ ፡ አስቀድሞ ፡
እንደ ፡ ነበሩ ፡ በሚገባ ፡ እግዚአብሔርንም ፡
እንደማያመልኩት ፡ በቀና ፡ ሕጉም ፡ ጸንተው ፡
እንዳላመኑ ፡ ወንጀለኞች ፡ ከእግዚአብሔር ፡
ሥልጣን ፡ የምታመልጥበት ፡ የለም ።
፲፪፤ ሁሉ ፡ በፊቱ ፡ ፈጽሞ ፡ የተገለጠ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡
ከፊቱ ፡ የሚሠወር ፡ የለም ።
፲፫፤ የነገሥታቱን ፡ ሥልጣን ፡ የሚይዝ ፡ የኃይለኞ
ችንም ፡ ዙፋን ፡ የሚገለብጥ ፡ እሱ ፡ ነው ።
፲፬፤ የተዋረዱትን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ የሚያደርግ ፡ የወደ
ቁትንም ፡ የሚያነሣ ፡ እሱ ፡ ነው ።
፲፭፤ የታሠሩትን ፡ የሚፈታ ፡ የሞቱትንም ፡ የሚያ
ስነሣ ፡ እሱ ፡ ነው ፡ የይቅርታ ፡ ጠል ፡ ከሱ ፡
ዘንድ ፡ ይገኛልና ፡ ሥጋቸው ፡ የፈረሰ ፡ የበሰ
በሰ ፡ እንደ ፡ ትቢያም ፡ የሆነ ፡ ሰዎችን ፡ በወ
ደደ ፡ ጊዜ ፡ ያስነሣቸዋል ።
፲፮፤ አሳዝነውታልና ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ የሠሩ ፡ ሰዎች
ንም ፡ አስነሥቶ ፡ ፈርዶ ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡ ይወስዳ
ቸዋል ።
፲፯፤ እነሳቸው ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሥራቱንና ፡
ሕጉን ፡ ያፈረሱ ፡ ናቸውና ፡ በዚህ ፡ ዓለምም ፡
ልጃቸውን ፡ ያጠፋል ።
፲፰፤ ከኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ ሥራ ፡ የደጋጎች ፡ ሰዎች ፡
ሥራ ፡ ጭንቅ ፡ ነውና ፡ ኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡
በደጋጎች ፡ ሰዎች ፡ ምክር ፡ ይኖሩ ፡ ዘንድ ፡ አይ
ወዱም ።
፲፱፤ ሰማይ ፡ ከምድር ፡ የራቀ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እንደ
ዚሁ ፡ የደጋጎች ፡ ሰዎች ፡ ሥራ ፡ ከኃጢአተኞች ፡
ሰዎች ፡ ሥራ ፡ የራቀ ፡ ነው ።
፳፤ የኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ ሥራ ፡ ግን ፡ የቅሚ
ያና ፡ የኃጢአት ፡ የዝሙትና ፡ የበደል ፡ የስስ
ትና ፡ የክዳት ፡ ሥራ ፡ ነው ፡ በበደል ፡ መስከ
ርና ፡ የሰውን ፡ ገንዘብ ፡ መቀማት ፡ ነው ።
፳፩፤ የሰውን ፡ ደም ፡ ወደ ፡ ማፍሰስ ፡ ፈጥኖ ፡ መሔድ ፡
ነው ፡ ወደማይጠቅም ፡ ጥፋትም ፡ መሔድ ፡
ነው ፡ እናት ፡ አባቱ ፡ የሞቱበት ፡ ልጅንም ፡ ማስ
ለቀስ ፡ ነው ፡ ደምና ፡ ሞቶ ፡ ያደረውን ፡ መብ
ላት ፡ ነው ፡ የግመልና ፡ የሪያም ፡ ሥጋ ፡ መብ
ላት ፡ ነው ፡ ሳትነጻ ፡ በደሟ ፡ ወዳለች ፡ ሴትና ፡
ወደ ፡ አራስ ፡ ሴትም ፡ መሔድ ፡ ነው ።
ይህ ፡ ሁሉ ፡ የኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ ሥራ ፡ ፳፪፤
ነው ፡ የሰሩች ፡ የተዘረጋች ፡ ጐዳና ፡ የምት
ሆን ፡ ዘላለም ፡ ፀንቶ ፡ ወደሚኖር ፡ ወደ ፡ ገሃነ
ምና ፡ ወደ ፡ ሲኦል ፡ የምትወስድ ፡ የሰይጣን ፡
ወጥመድ ፡ ናት ።
ፈጽማ ፡ ጠባብ ፡ የምትሆን ፡ የጻድቃን ፡ ጐዳና ፡ ፳፫፤
ግን ፡ ወደ ፡ ደኅንነት ፡ ወደ ፡ የዋሀነትና ፡ ወደ ፡
ትሕትናም ፡ ወደ ፡ አንድነትና ፡ ወደ ፡ ፍቅርም ፡
ወደ ፡ ጸሎትና ፡ ወደ ፡ ጾምም ፡ ወደ ፡ ሥጋም ፡
ንጽሕና ፡ ከማይጠቅም ፡ ሰይፍ ፡ ንሮ ፡ የቈረጠ
ውንና ፡ ሙቶ ፡ ያደረውን ፡ ከመብላት ፡ ወደ ፡
ጉልማሳ ፡ ሚስት ፡ ከመሄድና ፡ ከዝሙትም ፡
ወደ ፡ መጠበቅ ፡ የምትወስድ ፡ ናት ።
ኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ ይኸን ፡ ሁሉ ፡ ያደርጋ ፳፬፤
ሉና ፡ በሕግ ፡ ከልታዘዘ ፡ የሚያጸይፍ ፡ መብልን ፡
ከመብላትና ፡ ከተጠላ ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ከማይወደውም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ይጠበ
ቃሉ ።
ደጋግ ፡ ሰዎችስ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከማይወደው ፡ ፳፭፤
ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ይርቃሉ ።
ይወዳቸዋል ፡ ከመከራቸውም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ፳፮፤
አደራ ፡ ገንዘብ ፡ ይጠብቃቸዋል ።
ሥርዓቱንና ፡ ሕጉን ፡ የሚወደውንም ፡ ሁሉ ፡ ፳፯፤
ይጠብቃሉና ፡ ኃጢአተኞች ፡ ሰዎችን ፡ ግን ፡
ሰይጣን ፡ ይገዛቸዋል ።

ምዕራፍ ፡ ፲ ።

የፈጠራችሁን ፡ እስከ ፡ ዛሬም ፡ ድረስ ፡ የጠበ ፩፤
ቃችሁን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፍሩት ፡ እንጂ ፡
እናንተ ፡ መኳንንቱና ፡ ነገሥታቱ ፡ በሰይጣን ፡
ጎዳና ፡ አትሂዱ ።
ሁሉን ፡ በሚገዛ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ሕግና ፡ ትእ ፪፤
ዛዝ ፡ ፀንታችሁ ፡ ኑሩ ፡ እንጂ ፡ በሰይጣን ፡ ጎዳና ፡
አትሒዱ ።
የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ የኬጤዎንና ፡ የከናኔዎን ፡ ፫፤
የፌርዜዎንንም ፡ አገር ፡ ይወርሱ ፡ ዘንድ ፡
ወደ ፡ አማሌቅ ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ የሴፎር ፡
ልጅ ፡ ባላቅ ፡ በለዓምን ።
አንተ ፡ የረገምኸው ፡ የተረገመ ፡ የመረቅኸ ፬፤
ውም ፡ የተመረቀ ፡ ነውና ፡ ትረግምልኝ ፡ ዘንድ ፡
ረግመህ ፡ ታጠፋልኝ ፡ ዘንድ ፡ እኔም ፡ የሚያከብ
ርህን ፡ ብዙ ፡ ብርና ፡ ወርቅ ፡ እሰጥሃለሁ ፡ ብሎ
ታልና ፡ በሰይጣን ፡ መንገድ ፡ አትሒዱ ።
በለዓምም ፡ የጥንቆላውን ፡ ዋጋ ፡ አለኝታ ፡ አድ ፭፤
ርጎ ፡ መጥቷልና ፡ የሴፎር ፡ ልጅ ፡ ባላቅም ፡
የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ የሰፈሩበትን ፡ በታ ፡
አሳይቶታልና ።
ሟርቱን ፡ አድርጓልና ፡ መሥዋዕቱንም ፡ ሠው ፮፤
ቷልና ፡ ከሰባት ፡ ላሞችንና ፡ በጎችን ፡ አርዷ
ልና ፡ የእስራኤልንም ፡ ልጆች ፡ ረግሞ ፡ ያጠፋ ፡
ዘንድ ፡ ወዷልና ።
እርግማንን ፡ ወደ ፡ ምርቃት ፡ መለሳት ፡ እንጂ ፡ ፯፤
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ በቃሉ ፡ ይረግማቸው ፡

ዘንድ ፡ አልወደደምና ፡ በሰይጣን ፡ መንገድ ፡
አትሒዱ ።
፰፤ አንተ ፡ እግዚአብሔር ፡ የመረጠው ፡ ወገን ፡
ነህና ፡ ከሰማይ ፡ የሚመጣ ፡ የእግዚአብሔር ፡
ማደሪያ ፡ ነህና ፡ የሚረግሙህ ፡ ሰዎች ፡ የተረ
ገሙ ፡ ይሁኑ ፡ የሚመርቁህም ፡ የተመረቁ ፡ ይሁኑ ፡
አለ ።
፱፤ በፊቱ ፡ በመረቃቸው ፡ ጊዜ ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡
የሴፎር ፡ ልጅ ፡ ባላቅ ፡ አዘነ ፡ ፈጽሞም ፡ ተቈጣ ፡
ይረግማቸውም ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ።
፲፤ እግዚአብሔር ፡ የመረቀው ፡ ወገን ፡ ወደዚህ ፡
አገር ፡ መጥቷልና ፡ በለዓምም ፡ እግዚአብሔር ፡
የመረቃቸው ፡ እስራኤልን ፡ እኔ ፡ አልረግምም ፡
አለው ።
፲፩፤ የሴፎር ፡ ልጅ ፡ ባላቅም ፡ በለዓምን ፡ እኔስ ፡ ትረ
ግምልኝ ፡ ዘንድ ፡ ወድጄ ፡ ነበር ፡ በፊቴ ፡ መረ
ቅካቸው ፡ እንጂ ፡ አንተ ፡ ግን ፡ አልረገምካቸው ፡
ረግመህልኝ ፡ አንተ ፡ ስጠኝ ፡ ብትለኝ ፡ እኔስ ፡
ቤት ፡ ሙሉ ፡ ብርና ፡ ወርቅ ፡ በሰጠሁህ ፡ ነበር ፡
አንተ ፡ ግን ፡ ፈጽመህ ፡ መረቅካቸው ፡ ለኔም ፡
በጎ ፡ ነገር ፡ አላደረግህም ፡ እኔም ፡ ላንተ ፡ በጎ ፡
ነገር ፡ አላደርግም ፡ አለው ።
፲፪፤ በለዓም ፡ እግዚአብሔር ፡ ባንደበቴ ፡ ተናገር ፡
ያለኝን ፡ እሱን ፡ እናገራለሁ ፡ እንጂ ፡ እኔስ ፡ የእ
ግዚአብሔርን ፡ ነገር ፡ ቸል ፡ ብዬ ፡ መደፋፈር ፡
አልችልም ።
፲፫፤ የተመረቀ ፡ ወገንን ፡ እንዳልረግም ፡ ገንዘብን ፡
ብወድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይቈጣኛልና ፡ እኔስ ፡
ከነፍሴ ፡ ገንዘብን ፡ አልወድም ፡ አለ ።
፲፬፤ እግዚአብሔር ፡ አባታቸው ፡ ያዕቆብን ፡ የሚመ
ርቁህ ፡ ሰዎች ፡ የተመረቁ ፡ ይሁኑ ፡ የሚረግሙ
ህም ፡ ሰዎች ፡ የተረገሙ ፡ ይሁኑ ፡ ብሎታልና ፡
የተመረቀ ፡ ያዕቆብን ፡ እንዳልረግም ፡ እኔስ ፡
ከነፍሴ ፡ ገንዘብን ፡ አልወድም ፡ አለ ፡ የሚመር
ቅህም ፡ የተመረቀ ፡ ነው ።
፲፭፤ ያለ ፡ ፍርድም ፡ የሚረግምህ ፡ ሰው ፡ የተረገመ ፡
ነው ፡ ብሎታልና ፡ እግዚአብሔር ፡ አንተን ፡
ይወድህ ፡ ዘንድ ፡ ጐዳናህንና ፡ ሥራህን ፡ አቅና
ው ።
፲፮፤ እግዚአብሔርን ፡ በኃጢአታቸው ፡ እንዳሳዘ
ኑት ፡ እሱም ፡ ቸል ፡ እንዳላቸው ፡ እንደቀደሙ ፡
ሰዎችም ፡ አትሁን ፡ በጥፋት ፡ ውሀም ፡ ያጠፋ
ቸው ፡ አሉ ።
፲፯፤ በጠላቶቻቸውም ፡ እጅ ፡ ያጠፋቸው ፡ አሉ ፡
መከራ ፡ ያፀኑባቸው ፡ ክፉዎች ፡ ሰዎች ፡ የሆኑ ፡
ጠላቶችን ፡ አምጥቶ ፡ በጠላቶቻቸው ፡ እጅ ፡
ያጠፋቸው ፡ አሉ ፡ ጌቶቻቸውንም ፡ ከካህናቶ
ቻቸውና ፡ ከነቢያቶቻቸው ፡ ጋራ ፡ ማረኳቸው ።
፲፰፤ ወደማያውቁት ፡ ወደ ፡ ባዕድም ፡ አገር ፡ አደረሷ
ቸው ፡ ፈጽመው ፡ ማረኳቸው ፡ ከብቶቻቸው
ንም ፡ ዘረፉባቸው ፡ አገራቸውንም ፡ አጠፉ ።
፲፱፤ የከበረች ፡ አገር ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ አጥፍተንና ፡
ቅጥሯን ፡ አፍርሰዋልና ፡ ኢየሩሳሌምንም ፡
እንደ ፡ እርሻ ፡ አደረጓት ።

ካህናቱም ፡ ተማረኩ ፡ ሕጉም ፡ ፈረሰ ፡ አርበኞ ፳፤
ችም ፡ በጦር ፡ ተወግተው ፡ ወደቁ ።
በልቴቶችም ፡ ተማረኩ ፡ ተማርከዋልና ፡ ለራሳ ፳፩፤
ቸው ፡ አለቀሱ ፡ እንጂ ፡ ለሞቱ ፡ ለባሎቻቸው ፡
አላለቀሱም ።
ልጆቹም ፡ አለቀሱ ፡ ሽማግሎችም ፡ አፈሩ ፡ ለሽበ ፳፪፤
ታም ፡ ሰውና ፡ ለሽማግሌም ፡ አልራሩም ።
በገራቸው ፡ ያገኙትን ፡ ሁሉ ፡ አጠፉ ፡ እንጂ ፡ ፳፫፤
ለቆንጆዎችና ፡ በሕግ ፡ ላሉ ፡ አልራሩም ፡ ማደ
ሪያው ፡ ቤተ ፡ መቅደስን ፡ አስቀድሞ ፡ ያፈርስ ፡
ዘንድ ፡ በወደደ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወገኖ
ቹን ፡ ተቈጥቷልና ፡ ወደማያውቀት ፡ አገር ፡
ወደ ፡ አሕዛብ ፡ ማርከው ፡ ወሰዷቸው ።
ሁለጊዜ ፡ ፈጣሪያቸውን ፡ ያሳዝኑታልና ፡ ስለ ፳፬፤
ዚህ ፡ ነገር ፡ እግዚአብሔር ፡ የእስራኤልን ፡
ልጆች ፡ ቸል ፡ ባላቸው ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡
ኢየሩሳሌምን ፡ እንደርሻ ፡ እንድትታረስ ፡ አደ
ረጋት ።
ስላባቶቻቸው ፡ ይራራላቸዋልና ፡ እሱ ፡ ግን ፡ ፳፭፤
አንድ ፡ ጊዜ ፡ አላጠፋቸውም ፡ በውነት ፡ የነ
ገሡ ፡ በፈጣሪያቸውም ፡ ፊት ፡ በቀና ፡ ሕግ ፡ ፀን
ተው ፡ የኖሩ ፡ አባቶቻቸውን ፡ ይስሐቅና ፡ አብ
ሃምን ፡ ያዕቆብንም ፡ ይወዳቸዋልና ፡ ስለ ፡ አባ
ቶቻቸው ፡ ደግነት ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ይቅር ፡ የሚ
ላቸው ፡ ስለ ፡ ራሳቸው ፡ ደግነት ፡ አይደለም ።
እሱም ፡ እጥፍ ፡ በሆነ ፡ ክብር ፡ ላይ ፡ ሾማቸው ፡ ፳፮፤
በምድርና ፡ በሰማይም ፡ ሁለት ፡ መንግሥትን ፡
አገኙ ።
በሚያልፍ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ የምትኖሩ ፡ እናን ፳፯፤
ተም ፡ መኳንንቱና ፡ ነገሥታቱ ፡ በሚገባ ፡ ሥራ ፡
ጸንተው ፡ የኖሩ ፡ ከናንተ ፡ አስቀድሞ ፡ የነበሩ ፡
አባቶቻችሁ ፡ እንደዚሁ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያ
ትን ፡ እንደ ፡ ወረሱ ፡ ስማቸውም ፡ ለልጅ ፡
ልጅ ፡ ያማረ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አስቧቸው ።
መንግሥትህን ፡ ያቀናልህ ፡ ዘንድ ፡ ባማረ ፡ አነ ፳፰፤
ዋወራቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንዳገለገሉት ፡
ካንተ ፡ አስቀድሞ ፡ እንደ ፡ ነበሩ ፡ እንደ ፡ ደጋ
ጎች ፡ ነገሥታት ፡ ስምህ ፡ በበጎ ፡ አጠራር ፡
ይጠራ ፡ ዘንድ ፡ አንተም ፡ ሥራህን ፡ አቅና ።

ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

በትሕትናውና ፡ በጸሎቱ ፡ ይህን ፡ ያህል ፡ ወገ ፩፤
ንን ፡ ሲጠብቅ ፡ ያልተበሳጨ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡
ስንኳ ፡ ያላጠፉ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ባርያ ፡
ሙሴን ፡ አስበው ፡ አንተን ፡ በድለዋልና ፡ አቤቱ ፡
ወገኖችህን ፡ ይቅር ፡ በል ፡ ቸል ፡ አትበል ፡ እያለ ፡
ላሙት ፡ እግዚአብሔርም ፡ ያጠፋቸው ፡ ዘንድ ፡
ለወደደ ፡ ለእኅቱና ፡ ለወንድሙ ፡ በየዋህነቱ ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለምኖ ፡ ኃጢአታቸውን ፡
አስተሰረየላቸው ፡ እንጂ ፡ ያልተበሳጨ ፡ የእግ
ዚአብሔር ፡ አገልጋይ ፡ ሙሴን ፡ አስበው ።
አንተን ፡ በድያለሁና ፡ ኃጢአተኛ ፡ የምሆን ፡ ፪፤
እኔን ፡ ባርያህንም ፡ ይቅር ፡ በለኝ ፡ አንተ ፡
መሐሪ ፡ ነህና ፡ ይቅር ፡ ባይም ፡ ነህና ፡ እነሳቸው

ንም ፡ ኃጢአታቸውን ፡ ይቅር ፡ በላቸው ።
፫ ሙሴም ፡ ሳሙኤል ፡ ለእኅቱና ፡ ለወንድሙ ፡ እን
ደዚሁ ፡ ኃጢአታቸውን ፡ አስተሰረየላቸው ።
፬ ስለዚህም ፡ ነገር ፡ የዋህን ፡ ተባለ ።
፭ እግዚአብሔርም ፡ ወንድሞቹ ፡ ከሆኑ ፡ ከካህ
ናቱ ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ፈጽሞ ፡ ወደደው ፡
ከሀናቱን ፡ ይሾማቸዋልና ፡ በነሳቸውም ፡ ዘንድ ፡
እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ራሱ ፡ አደረገው ።
፮ የተደፋፈሩ ፡ የቆሬንም ፡ ልጆች ፡ ግን ፡ በምድ
ር ፡ በታች ፡ አሰጠማቸው ፡ ከኩብቶቻቸውና ፡
ከድንኳኖቻቸው ፡ ጋራ ፡ በሥጋና ፡ በነፍስ ፡
አለን ፡ አለን ፡ ሲሉ ፡ ወደ ፡ሲኦል ፡ አወረዳ
ቸው ፡ ፈጣሪው ፡ እግዚአብሔር ፡ ወዮታልና ፡
ከትእዛዙም ፡ አልወጣምና ፡ የተናገረው ፡ ቃል ፡
ሁሉ ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ይደረግ
ለት ፡ ነበር ።
፯ አንተም ፡ እንደዚሁ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ትእ
ዛዝ ፡ ካላፈረስህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፈቃድህን ፡
ያደርግልሃል ፡ ነገርህንም ፡ ይወድልሃል ፡ መን
ግሥትህንም ፡ ይጠብቅልሃል ።
፰ ከሙሴ ፡ ትእዛዝ ፡ የወጡ ፡ የአሳፍና ፡ የቆሬም ፡
ልጆች ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ልትገዙ ፡ ልቡናች
ሁን ፡ አቅኑ ፡ ሰላላቸው ፡ በሱ ፡ አንጐራጐሩ ።
፱ እኛስ ፡ በልዩ ፡ በሆነች ፡ ድንኳን ፡ የክህነት ፡
ሥራ ፡ የምንሠራ ፡ የሌዊ ፡ ልጆችን ፡ አይደለን
ምን ፡ ብለው ፡ አንጐራጐሩ ።
፲ ያጥኑ ፡ ዘንድ ፡ ጥናቸውን ፡ ይዘው ፡ ሄደው ፡
አጠኑ ፡ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ልመናቸውን ፡
አልተቀበለም ፡ በጥናቸው ፡ ባለ ፡ እሳትም ፡ ተቃ
ጠሉ ፡ እሳት ፡ እንደሚያቀልጠው ፡ ሰምም ፡
ቀለጡ ፡ ከነሳቸው ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ስንኳ ፡ አል
ቀረም ፡ በሰውነታቸው ፡ መቃጠል ፡ ጥናቸው ፡
ኩብሯል ፡ ብዓልና ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ትእዛዝ ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ ከገቡት ፡ ከጥና
ቸው ፡ በቀር ፡ ልብሶቻቸውና ፡ አጥንቶቻቸ
ውም ፡ አልቀሩም ።
፲፩ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ እግዚአብሔር ፡ አሮንና ፡ ሙሴን ፡
ጥናቸውን ፡ ወደ ፡ ድንኳን ፡ ሰብስቡ ፡ ከውጪ ፡
ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ውስጥ ፡ ድረስ ፡ ሁሉን ፡ ላዘጋ
ጀሁለት ፡ ማደሪያዬ ፡ መሠሪያ ፡ ይሁን ፡ አላቸው ።
፲፪ የከበረች ፡ የድንኳኑንም ፡ መሠርያ ፡ አዘጋጀ ፡
ቀለበቱንና ፡ መግጠሚያውን ፡ የኪሩቤልን ፡
ሥዕል ፡ ባሕርን ፡ አዘጋጀ ።
፲፫ ስኑን ፡ መጋረጃውን ፡ ለክተቱን ፡ የድንኳኑን ፡
ዙሪያ ፡ ዕድሞ ፡ ልዩ ፡ በሆነ ፡ ድንኳን ፡ የሚሠ
ዉበት ፡ መሠዊያውንና ፡ ጋኑን ፡ ሠራ ።
፲፬ በፈቃዳቸው ፡ የሚሠውትን ፡ መሥዋዕት ፡ ድኅ
ነት ፡ የሚደረግበትን ፡ መሥዋዕተ ፡ ኃጢአት ፡
የሚያሥተሠርይበትን ፡ መሥዋዕት ፡ የስለቱ
ንም ፡ መሥዋዕት ፡ የማታውንና ፡ የጧቱንም ፡
መሥዋዕት ፡ ሠው ።
፲፭ ሥራ ፡ ይሠሩበት ፡ ዘንድ ፡ ልዩ ፡ በሆነች ፡ ድን
ኳን ፡ ለሙሴ ፡ ያዘዘውን ፡ ሁሉ ፡ አዘዛቸው ።
፲፮ ማርና ፡ ወተትን ፡ የምታስገኝ ፡ ለአብርሃም ፡ የማ
ለሉትን ፡ ያባቶቻቸውን ፡ ርስት ፡ እንዲሰጣቸው ፡
ይሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ ተስፋ ፡ በሰጣቸው ፡ በፈጣ
ሪያቸው ፡ በእግዚአብሔር ፡ በሕጉ ፡ ማደሪያ ፡
በድንኳን ፡ ስሙ ፡ በነሳቸው ፡ ይመሰገን ፡ ዘንድ ፡
ለፈጣሪያቸው ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መገዛትን ፡
አላቀለሉም ።
ለይስሐቅ ፡ የማለለት ፡ ለያዕቆብም ፡ አምልክ ፲፯
ቱን ፡ ያጸናለት ።
አምልኮቱ ፡ በሚጠበቅበት ፡ ድንኳንም ፡ ለአሮ ፲፰
ንና ፡ ለሙሴ ፡ ያጸናላቸው ።
በኢየሩሳሌም ፡ የእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ እስ ፲፱
ኪሆን ፡ ድረስ ፡ ሰሎሞን ፡ በሠራው ፡ ቤት ፡
መቅደስና ፡ በድንኳን ፡ የእግዚአብሔር ፡ የስሙ ፡
ማደሪያ ፡ እስራኤልን ፡ ያከበረ ፡ የእግዚአብሔ
ርም ፡ ማደሪያ ፡ እስኪሆን ፡ ድረስ ፡ ለኤልያስና ፡
ለሳሙኤልም ፡ አምልኮቱን ፡ ላጸናላቸው ፡ ለፈ
ጣሪያቸው ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መገዛትን ፡ አላ
ቃለሉም ።
መለመኛ ፡ ናትና ፡ በየዋህነት ፡ ለሚኖሩ ፡ ለካህ ፳
ናቱም ፡ የሚገለጥበት ፡ የኃጢአት ፡ ማስተሥ
ረያ ፡ ናትና ።
ፈቃዱንም ፡ ለሚያደርጉ ፡ ሰዎች ፡ ልመናቸ ፳፩
ውን ፡ የሚሰማበት ፡ ቦታ ።
እስራኤልን ፡ ያከበረ ፡ የእግዚአብሔር ፡ የሕጉ ፡ ፳፪
መሠሪያ ፡ ናትና ።
እስራልኤን ፡ ያከበረ ፡ እግዚአብሔር ፡ በን ፡ ፳፫
መዓዛ ፡ ሊሆን ፡ መሥዋዕት ፡ የሚሠዋበት ፡
ዕጣን ፡ የሚታጠንበት ፡ ናትና ።
ልዩ ፡ በሆነች ፡ በድንኳን ፡ ይቅር ፡ በሚልበት ፡ ፳፬
በመግጠሚያውም ፡ ላይ ፡ ሆኖ ፡ ይናገር ፡ ነበር ፡
ለመረጣቸው ፡ ለያዕቆብ ፡ ልጆች ፡ በሕጉና ፡
በትእዛዙ ፡ ፀንተው ፡ ለሚኖሩ ፡ ለወዳጆችም ፡
የእግዚአብሔር ፡ ብርሃኑ ፡ ይገለጥላቸው ፡ ነበር ።
የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ ቸል ፡ ያሉ ፡ ሰዎች ፡ ፳፭
ግን ፡ ምድር ፡ እንዳሰጠመቻቸው ፡ እንደ ፡ ቆሬ ፡
ልጆች ፡ ይሆናሉ ፡ ለኃጢአተኞችም ፡ ሰዎች ፡
እስከ ፡ ዘላለም ፡ ድረስ ፡ መውጫ ፡ ወደሌላት ፡
ወደ ፡ ገሃነም ፡ ይገቡ ፡ ዘንድ ፡ እንደዚሁ ፡ አላ
ቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

በድንኳን ፡ ያዘዛችሁን ፡ ሕጉን ፡ ያልጠበቃ ፩
ችሁ ፡ የራሳችሁን ፡ ፈቃድ ፡ አደረጋችሁ ፡ እንጂ ፡
ፈቃዱንም ፡ ያላደረጋችሁ ፡ የእስራኤል ፡ መኳ
ንንቶች ፡ ወዮላችሁ ፡ ይኸውም ፡ መታበይና ፡
ኩራት ፡ ስስትና ፡ ዝሙት ፡ መጠጥና ፡ መስከር ፡
በሐሰትም ፡ መማል ፡ ነው ።
ስለዚህም ፡ ነገር ፡ ቊጣዬ ፡ በእሳት ፡ ፊት ፡ ያለ ፡ ፪
ገለባ ፡ እንዲነድ ፡ እሳትም ፡ ተራራውን ፡ እንዲ
ያቃጥል ፡ ጥቅል ፡ ነፋስም ፡ የደቀቀውን ፡ ገለባ ፡
ከምድር ፡ አፍሶ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ እንዲበትነው ፡
ፍለጋው ፡ በቦታው ፡ እንደማይገኝ ፡ ቊጣዬ ፡
እንዲያ ፡ ያጠፋችኋል ።
እስራኤልን ፡ ያከበረ ፡ እግዚአብሔር ፡ ኃጢአ ፫

ትን ፡ የሚሠሯትን ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ እንደዚሁ ፡
አጠፋቸዋለሁ ፡ አለ ፡ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ የሚሳ
ነው ፡ የሌለ ፡ እግዚአብሐርንም ፡ አስቡት ።
፬፤ የሚወዱትን ፡ ሰዎች ፡ ይወዳቸዋል ፡ በትእዛ
ዙም ፡ ፀንተው ፡ ለሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ በደላቸው
ንና ፡ ኃጢአታቸውን ፡ ያስተሠርይላቸዋል ፡
በለማመን ፡ የልብ ፡ ደንቆሮዎችና ፡ ንፉጎችን ፡
አትሁኑ ።
፭፤ ለእግዚአብሔርም ፡ ልትገዙ ፡ ልቡናችሁን ፡
የቀና ፡ አድርጉ ፡ ሰውነታችሁንም ፡ ቃፀኑ ፡
ዘንድ ፡ በሱ ፡ እመኑ ፡ በመከራችሁም ፡ ቀን ፡
ከጠላታችሁ ፡ እጅ ፡ አድናችኋለሁ ።
፮፤ በለመናችሁኝም ፡ ጊዜ ፡ እነሆ ፡ ከናንተ ፡ ጋራ ፡
በረድኤት ፡ አለሁ ፡ እላችኋለሁ ፡ ከጠላታችሁ ፡
እጅ ፡ አድናችኋለሁ ፡ በኔ ፡ አምናችኋልና ፡ ትእ
ዛዜንም ፡ አድርጋችኋልና ፡ ከሕጌም ፡ አልወጣ
ችሁምና ፡ እኔ ፡ የምወደውንም ፡ ወዳችኋልና ፡
ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ እግዚአብሔር ፡ በመከራችሁ ፡
ቀን ፡ ቸል ፡ አልላችሁም ፡ አለ ።
፯፤ የሚወዱትን ፡ ይወዳቸዋል ፡ ይቅር ፡ ባይ ፡
ነውና ፡ ርኅሩኅም ፡ ነውና ፡ ሕጉንም ፡ የሚጠ
ብቁ ፡ ሰዎችን ፡ እንዳይደራ ፡ ገንዘብ ፡ ይጠብቃቸ
ዋል ።
፰፤ ቍጣውን ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ይመልስላቸዋል ፡
ሥጋዊ ፡ ደማዊ ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ የሚያውቃቸው ፡
ስለ ፡ ሆነ ፡ ይቅር ፡ ባይ ፡ ነውና ፡ በመቅሠፍቱ ፡
ሁሉ ፡ አያጠፉም ፡ ነፍሳቸውንም ፡ ከሥጋቸው ፡
በተለየች ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ መሬትነታቸው ፡ ይመ
ለሳሉ ።
፱፤ ከለመኖር ፡ ወደ ፡ መኖር ፡ አምጥቶ ፡ ፈጥሯቸ
ዋልና ፡ ከለመኖር ፡ ወደ ፡ መኖር ፡ ያመጣቸው ፡
ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ እስኪወድ ፡ ድረስ ፡
የሚኖሩበትን ፡ በታ ፡ አያውቋም ፡ ዳግመኛ ፡
እሱ ፡ ነፍሳቸውን ፡ ከሥጋቸው ፡ ለየ ፡ የመ
ሬት ፡ ባሕርይንም ፡ ወደ ፡ መሬትነቱ ፡ መለሰ ።
፲፤ ዳግመኛም ፡ ከለመኖር ፡ ፈቃዱ ፡ ወደ ፡ መኖር ፡
ያመጣቸዋል ።
፲፩፤ እግዚአብሔርን ፡ የካደ ፡ ጺሩጻይዳን ፡ ግን ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ መቃበይን ፡ አበዛ ፡ እስከ ፡
ወደደበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ በተወው ፡ ጊዜ ፡ ራሱን ፡
ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረገ ።
፲፪፤ ዘመኔም ፡ እንደ ፡ ሰማይ ፡ ዘመን ፡ ሆነ ፡ ፀሐይ
ንም ፡ የማወጣ ፡ እኔ ፡ ነኝ ፡ እስከ ፡ ዘላለምም ፡
ድረስ ፡ አልሞትም ፡ አለ ።
፲፫፤ ይህንንም ፡ ነገር ፡ ተናግሮ ፡ ሳይጨርስ ፡ ስሙ ፡
ጥልምያክስ ፡ የሚባል ፡ መልአክ ፡ ሞት ፡ ወርዶ ፡
ልቡን ፡ መታው ፡ በዚያችው ፡ ሰዓት ፡ ሞተ ፡
ፈጣሪውን ፡ አላመሰገነውምና ፡ ከትቢቱ ፡ ብዛት ፡
ከሥራውም ፡ ክፋት ፡ የተነሣ ፡ ካማረ ፡ አነዋ
ወሩ ፡ ተለይቶ ፡ ጠፋ ።
፲፬፤ የከለዳውያን ፡ ንጉሥ ፡ ሠራዊት ፡ ግን ፡ ሊወ
ጉት ፡ ወደው ፡ በከተማውና ፡ በገሩ ፡ አደባበይ ፡
ሰፍረው ፡ ሳሉ ፡ በሞተ ፡ ጊዜ ፡ ወጥተው ፡ አገ
ሩን ፡ አጠፉ ፡ ከብቱን ፡ ሁሉ ፡ ዘረፉ ፡ ቀጥር ፡
ተጠግቶ ፡ የሚያይ ፡ ሽማግሌም ፡ አላስቀሩም ።
ገንዘቡን ፡ ሁሉ ፡ ዘረፉ ፡ ጥቃቅን ፡ ገንዘቡንም ፡ ፲፭፤
ወሰዱ ፡ አገሩንም ፡ በእሳት ፡ አቃጥለው ፡ ወደ ፡
አገራቸው ፡ ተመለሱ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

ያመኑ ፡ እሊያ ፡ አምስቱ ፡ የመቃቢስ ፡ ልጆች ፡ ፩፤
ግን ፡ ለጣዖት ፡ የተሠዋውን ፡ መሥዋዕት ፡ መብ
ላት ፡ እምቢ ፡ ብለው ፡ ሰውነታቸውን ፡ ለሞት ፡
ሰጡ ።
ሰውን ፡ ከመገዳደር ፡ እግዚአብሔርን ፡ መገዳ ፪፤
ደር ፡ ከንጉሡም ፡ ቍጣ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡
እንዲበልጥ ፡ አውቀዋልና ።
ይህ ፡ ዓለም ፡ ፈጽሞ ፡ እንዲያልፍ ፡ ተድላ ፡ ደስ ፫፤
ታውም ፡ ለዘላለም ፡ ፀንቶ ፡ እንዳይኖር ፡ አው
ቀው ፡ በሰማይ ፡ ካለ ፡ እሳት ፡ ይድኑ ፡ ዘንድ ፡
ሰውነታቸውን ፡ ለሳት ፡ ሰጡ ።
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ ከመኖርም ፡ በገ ፬፤
ነት ፡ አንዲት ፡ ቀን ፡ ደስ ፡ መሰኘት ፡ እንዲሻል ፡
ከብዙ ፡ ዘመኖችም ፡ አቤቱ ፡ አንዲት ፡ ሰዓት ፡
ይቅርታህን ፡ ማግኘት ፡ እንዲሻል ፡ አውቀዋ
ልና ፡ ሰውነታቸውን ፡ ለሳት ፡ ሠጡ ።
የኛ ፡ ዘመን ፡ ምንድነው ፡ እንደ ፡ ጥላ ፡ የሚያ ፭፤
ልፍ ፡ በእሳት ፡ ዳር ፡ ያለ ፡ ሰም ፡ ቀልጦ ፡ እንዲ
ጠፋ ፡ እንደዚያ ፡ አይደለምን ።
አቤቱ ፡ አንተ ፡ ግን ፡ ለዘላለሙ ፡ ትኖራለህ ፡ ዘመ ፮፤
ንህም ፡ የማይፈጸም ፡ ነው ፡ ስም ፡ አጠራርህም ፡
ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ነው ።
የመቃቢስ ፡ ልጆች ፡ ይኸን ፡ ሁሉ ፡ የሚመስለ ፯፤
ውንም ፡ ሁሉ ፡ አሰቡ ፡ የሚያጸይፍ ፡ መሥዋዕ
ትን ፡ መብላት ፡ እምቢ ፡ ብለው ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ መታመንን ፡ መረጡ ።
ከሞቱ ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ እንዲነሡ ፡ አውቀው ፡ ፰፤
ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ብለው ፡ ከትንሣኤ ፡ ዘጉ
ባዔ ፡ በኋላም ፡ ፍርድ ፡ እንዲፈረድ ፡ አውቀው ፡
ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ሰውነታቸውን ፡ ለሰማዕትነት ፡
ሰጡ ።
የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ መነሣትን ፡ የማታውቁና ፡ የማ ፱፤
ታምኑ ፡ ሰዎች ፡ ከዚህች ፡ ከምታልፍ ፡ ከምድራ
ዊት ፡ ሕይወታቸው ፡ ኋላ ፡ የሚያገኟት ፡ ሕይ
ወት ፡ እንድትበልጥ ፡ አውቀው ፡ ሰውነታቸ
ውን ፡ አንድነት ፡ ለሞቱ ፡ ከሠጡ ፡ መልከቸው ፡
ካማረ ፡ ከነዚህ ፡ ከምስቱ ፡ ከመቃቢስ ፡ ልጆች ፡
የተነሣ ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ትንሣኤን ፡ አወቁ ።
ሁሉ ፡ እንዲያልፍ ፡ አውቀው ፡ ስላመኑበት ፡ ፲፤
ለጣዖትም ፡ ስላልሰገዱ ፡ ረድኤት ፡ ከማታሰጥ ፡
ከምታጸይፍ ፡ መሥዋዕት ፡ ስላልበሉ ፡ ከእግዚ
አብሔር ፡ ምስጋናን ፡ ያገኙ ፡ ዘንድ ፡ ሰውነታቸ
ውን ፡ ለሞት ፡ ሰጡ ።
ስለዚህ ፡ ነገር ፡ በሥጋና ፡ በነፍስ ፡ በኋላ ፡ ዘመን ፡ ፲፩፤
ደስ ፡ እንዲያሰኛቸው ፡ አውቀው ፡ ልጅና ፡
ሚስት ፡ ላላቸው ፡ የዚህን ፡ ዓለም ፡ ጣዕም ፡
የሞትንም ፡ መከራ ፡ ቁም ፡ ነገር ፡ አላወቁምና ፡
በዕለት ፡ ምጽአትም ፡ በሥጋና ፡ በነፍስ ፡ ትን

ማኤ ፡ እንዲደረግ ፡ አውቀው ፡ ሰውታቸውን ፡
ለሞት ፡ ሠጡ ።
፲፪፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ የጠበቁ ፡ ሰዎች ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ከመኑ ፡ ደጋግ ፡ ከሆኑ ፡
ከመኳንንቱና ፡ ከነገሥታቱ ፡ ጋራ ፡ ኀዘንና ፡
መከራ ።
፲፫፡ ሞት ፡ በሴለበት ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ በመንግሥት ፡
ሰማይ ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ነግሠው ፡ እንዲኖሩ ፡
አውቀው ፡ ኋላም ፡ የሚደረገውን ፡ በልቡና
ቸው ፡ አውቀው ፡ በእሳት ፡ መከከል ፡ ያለ ፡ ሰም ፡
እንዲቀልጥ ፡ ስለዚህም ፡ ነገር ፡ ሰውነታቸውን ፡
ለሞት ፡ ሰጡ ።
፲፬፡ ሬታቸው ፡ ከፀሐይ ፡ ሰባት ፡ እጅ ፡ እንዲያበሩ ፡
ሁሉ ፡ በሥጋና ፡ በነፍስ ፡ በትንሣ ፡ ጊዜ ፡ በፍ
ቅሩ ፡ ደስ ፡ እንዲላቸው ፡ አምነው ፡ ሰውነታቸ
ውን ፡ ለሞት ፡ ሰጡ ።

ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

፩፡ የሳምራውያንና ፡ የአይሁድ ፡ ነገር ፡ የሞቱ ፡
ሰዎች ፡ መነሣትን ፡ የማያምኑ ፡ የሰዱቃውያ
ንና ፡ የፈሪሳውያን ፡ ነገር ፡ እኔን ፡ ግን ፡ ፈጽሞ ፡
እጅግ ፡ ያሳዝነኛል ፡ ለልቡናዬም ፡ ይረዳኛል ፡
ነገ ፡ እንሞታለን ፡ አይሁድ ፡ እንብላ ፡ እንጠጣ ፡
ነገ ፡ እንሞታለን ፡ በመቃብር ፡ የምናየው ፡ ተድላ ፡
ደስታ ፡ የለም ፡ ይላሉ ።
፪፡ ሳምራውያን ፡ ግን ፡ ሥጋችን ፡ ትቢያ ፡ ይሆና
ልና ፡ አይነሣም ፡ ይላሉ ።
፫፡ እንደ ፡ ነፋስ ፡ የማትታይ ፡ እንደ ፡ ነጐድጓድም ፡
ድምፅ ፡ ስለ ፡ ሆነች ፡ እነሆ ፡ እዚህ ፡ አለች ፡ የማ
ይሏት ፡ የማትታይም ፡ ስለ ፡ ሆነች ፡ ሥጋ ፡ ቢሞት ፡
ነፍስ ፡ አትሞትምና ፡ ትንሣኤ ፡ በተደረገ ፡ ጊዜ ፡
የነፍሳችንን ፡ መነሣት ፡ እናምናለን ።
፬፡ አውሬዎች ፡ ይበሏታልና ፡ ትሎችም ፡ በመቃ
ብር ፡ ይበሏታልና ፡ ሥጋችን ፡ ግን ፡ በሁሉ ፡
ዘንድ ፡ ትታያለች ፡ ትቢያና ፡ አመድ ፡ ትሆና
ለች ።
፭፡ እንደ ፡ ሣር ፡ ሆነዋልና ፡ እንዳልተፈጠሩም ፡
ትቢያ ፡ ሆነዋልና ፡ እነዚያም ፡ የበሏት ፡ አውሬ
ዎች ፡ ትቢያ ፡ ይሆናሉ ፡ ፍለጋቸውም ፡ አይገኝ
ምና ፡ ሥጋችን ፡ ግን ፡ አይነሣም ።
፮፡ ፈሪሳውያንም ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ መነሣትንስ ፡
እናምናለን ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ነፍሳትን ፡ በምድር ፡
ያይደለ ፡ በሰማይ ፡ ሌላ ፡ ሥጋ ፡ አምጥቶ ፡ ያዋ
ሕዳቸዋል ፡ የፈረሱ ፡ የበሰበሱ ፡ ሥጋዎች ፡
ወዴት ፡ ይገኛሉ ፡ ይላሉ ።
፯፡ ሰዱቃውያን ፡ ግን ፡ ነፍሳችን ፡ ከሥጋችን ፡ ከወ
ጣች ፡ በኋላ ፡ ከሞቱ ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ አንነሣም ፡
ለሥጋና ፡ ለነፍስም ፡ ከሞቱ ፡ በኋላ ፡ መነሣት ፡
የላቸውም ፡ ከሞትንም ፡ በኋላ ፡ አንነሣም ፡
ይላሉ ።
፰፡ ስለዚህም ፡ ነገር ፡ ፈጽመው ፡ ይስታሉ ፡ በእግ
ዚአብሔርም ፡ በጌትነቱ ፡ ላይ ፡ ስድብን ፡ ይናገ
ራሉና ፡ የነሳቸው ፡ ነገር ፡ ያሳዝነኛል ።
፱፡ የሚያከብሩቸው ፡ እግዚ አብሔርን ፡ አላመኑት
ምና ፡ ለመዳን ፡ ተስፋ ፡ የላቸውም ፡ ነገር ፡ ግን ፡
ሞቶ ፡ ለመነሣትና ፡ ለመዳንም ፡ ተስፋ ፡ የላቸ
ውም ።
የልቡና ፡ ዕውር ፡ የምትሆን ፡ አይሁዳዊ ፡ ሆይ ፡ ፲፡
ከለመኖር ፡ ወደ ፡ መኖር ፡ አምጥቶ ፡ የፈጠረህን ፡
እንደ ፡ ምራቅም ፡ የተናቅህ ፡ ስትሆን ፡ ሰው ፡
ያደረገህ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አላዋቂ ፡ ታደርገ
ዋለህን ፡ በምሳሌውና ፡ በመልኩ ፡ የፈጠረህ ፡
እግዚአብሔር ፡ ሥጋህንና ፡ ነፍስህን ፡ አዋሕዶ ፡
ማስነሣት ፡ ይሳነዋልን ።
ከእግዚአብሔር ፡ ሥልጣን ፡ አታመልጥምና ፡ ፲፩፡
እንዲህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ አታስብ ፡ ሳትወድ ፡ ትነሣ
ለህ ፡ በሞትህ ፡ ጊዜ ፡ የተያዝህበት ፡ በሲኦል ፡
የምትቀበለው ፡ ፍዳ ፡ በሰውነትህ ፡ አለና ፡ ሳት
ወድም ፡ ይፈረድብሃል ።
ከአጋንንት ፡ የምትገኝ ፡ አጋንንት ፡ በልቡናህ ፡ ፲፪፡
የሚያኖሯት ፡ ኃጢአት ፡ ከናትህ ፡ ማኅፀን ፡ ከተ
ወለድህ ፡ በኋላ ፡ ባንተ ፡ ዘንድ ፡ ትሠራለችና ፡
አንተ ፡ በደግህ ፡ ጊዜ ፡ እሷም ፡ በዝታ ፡ ትሠራ
ለችና ።
አንተ ፡ በሞትህ ፡ ጊዜ ፡ በሰውነትህ ፡ ያኖረታል ፡ ፲፫፡
በሠራትም ፡ ጊዜ ፡ እሷ ፡ ፍዳ ፡ ታመጣበቸዋ
ለች ።
በክፋደ ፡ ልቡናቸው ፡ ኃጢአት ፡ እንዳለ ፡ ኃጢ ፲፬፡
አት ፡ የሚሠሩ ፡ ሰዎች ፡ በሷ ፡ ተይዘው ፡ አሉና ፡
ወገኖቿ ፡ አጋንንትን ፡ ታቀርባለች ።
የኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ ነፍሳት ፡ ሁሉ ፡ ካሉ ፲፭፡
በት ፡ ከሰማይ ፡ ዳርቻ ፡ ይመጣሉ ፡ ኃጢአትህም ፡
እንደዚሁ ፡ ነፍስህን ፡ ካለህበት ፡ ስባ ፡ አምጥታ ፡
ወደ ፡ ገሃነም ፡ ታገባሃለች ።
ሥጋህም ፡ ከነፍስህ ፡ ተለይታ ፡ ከኖረ ፡ በኋላ ፡ ፲፮፡
እንዳባታችን ፡ እንደ ፡ አዳም ፡ ሥጋ ፡ ሰባት ፡
እጥፍ ፡ ሆኖ ፡ የእግዚአብሔር ፡ የቸርነቱ ፡ ጠል ፡
ታስነሣሃለች ፡ ኃጢአትና ፡ በደልን ፡ እንደ ፡
ሠራህ ፡ እንዳላመንህ ፡ በዚያ ፡ ፍዳህን ፡ ትቀበ
ላለህ ።
በመቃብር ፡ የምትኖር ፡ አንተ ፡ በስተትህ ፡ አን ፲፯፡
ተም ፡ ትስታለህ ፡ እንጂ ፡ ሌላውን ፡ ብቻ ፡ የም
ታስት ፡ አይምሰልህ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ትእዛዝ ፡
ወጥተው ፡ ይስቱ ፡ ዘንድ ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ የሚ
ነሡት ፡ መነሣት ፡ የለም ፡ ትላለህ ።
እንደ ፡ ሠራኸው ፡ ሥራህ ፡ ፍዳህን ፡ ይሰጥህ ፡ ፲፰፡
ዘንድ ፡ ያስነሣሃል ፡ እንጂ ፡ ትቢያ ፡ ሆነህ ፡ ትቀር ፡
ዘንድ ፡ ማን ፡ ይተውሃል ።
የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ በነፋስ ፡ ያለ ፡ ነፋስ ፡ በሕ ፲፱፡
ርይህም ፡ ቢሆን ፡ በውኃ ፡ ያለ ፡ ውኃ ፡ በሕርይ
ህም ፡ ቢሆን ፡ በመሬት ፡ ያለ ፡ መሬት ፡ በሕር
ይህም ፡ ቢሆን ፡ በእሳት ፡ ያለ ፡ እሳት ፡ በሕርይ
ህም ፡ ቢሆን ፡ ይመጣል ።
ባንተ ፡ ያደረች ፡ በሲኦል ፡ የምትኖር ፡ ነፍስም ፡ ፳፡
ብትሆን ፡ ትመጣለች ።
በገነት ፡ በደስታ ፡ የሚኖሩ ፡ የጻድቃን ፡ ነፍስ ፳፩፡
ችም ፡ ይመጣሉ ።
አይሁዳዊ ፡ ሳምራዊ ፡ ፈሪሳዊ ፡ ሰዱቃዊ ፡ አንተ ፡ ፳፪፡

ግን ፡ እስኪፈረድብህ ፡ ድረስ ፡ በሲኦል ፡ ትኖ
ራለህ ።
፳፫ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ሰውን ፡ ስለ ፡ አሳትህ ፡ እንደ ፡ ኃጢ
አትህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፍዳውን ፡ እንዲከፍልህ ፡
ታያለህ ።
፳፬ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ አይነሡም ፡ ነገ ፡ እንሞታለንና ፡
እንብላ ፡ እንጠጣ ፡ በሙሴም ፡ ወምበር ፡ ተቀም
ጠህ ፡ በቃልህ ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ አይነሡም ፡
እያልህ ፡ ስላሳትህ ፡ ፍዳህን ፡ እንዲከፍልህ ፡
ታያለህ ።
፳፭ የኦሪትን ፡ መጽሐፍ ፡ ሳታውቅ ፡ የመጻሕፍት
ንም ፡ ቃል ፡ ስታስተምር ፡ ስለዚህም ፡ ነገር ፡
ሳትህ ፡ ሰውን ፡ ከማሳትህ ፡ ሳትማር ፡ በቀረህ ፡
ይሻል ፡ ነበር ።
፳፮ በክፉ ፡ ትምህርትህ ፡ በማይረባ ፡ ቃልህ ፡ የእግ
ዚአብሔርን ፡ ወገን ፡ ስታስክድ ፡ የመጻሕፍት ፡
ቃል ፡ ባላወቅህ ፡ በተሻለህ ፡ ነበር ።
፳፯ እግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ አይቶ ፡ አያደላምና ፡ በጎ ፡
ሥራንም ፡ ለሚያስተምሩ ፡ ሰዎች ፡ ለወዳጆቹ ፡
ያዘጋጀውን ፡ ጸጋ ፡ ክብር ፡ ይሰጣቸዋልና ፡
አንተ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ሥራህ ፡ እንደ ፡ ተናገርከው ፡
ነገር ፡ ዋጋህን ፡ ትቀበል ፡ ዘንድ ፡ አለህ ።
፳፰ አንተ ፡ ግን ፡ ከሚፈርድብህ ፡ ከእግዚአብሔር ፡
ሥልጣን ፡ የምታመልጥበት ፡ የለም ፡ እንደ ፡
ሥራህም ፡ ይከፍልህ ፡ ዘንድ ፡ አለው ፡ ያስተማ
ርካቸውና ፡ አንተ ፡ አንድነት ፡ መቻያ ፡ ትቀበ
ላላችሁና ።
፳፱ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ እንዲነሡ ፡ እወቅ ፡ ሕጉንም ፡
የጠበቁ ፡ ሰዎች ፡ ቢሆኑ ፡ ይነሣሉ ፡ ዝናም ፡ በዘ
ነመ ፡ ጊዜ ፡ ምድር ፡ ሣርን ፡ እንድታወጣ ፡ ትእ
ዛዙ ፡ ከመቃብር ፡ ያወጣቸዋልና ፡ ፈርሶ ፡ በስ
ብሶ ፡ መቅረት ፡ አይቻለውም ።
፴ ለምድር ፡ ዝናምን ፡ በጠገበት ፡ ጊዜ ፡ ጠልን ፡
ጠጥታ ፡ የረጠበች ፡ እንጨት ፡ ቅጠልን ፡ እን
ድታወጣ ፡ ስንዴ ፡ ፍሬን ፡ እንድታፈራ ፡ እህ
ልም ፡ ዝርዝርን ፡ እንድታስገኝ ፡ እግዚአብሔር ፡
ከወደደ ፡ ፍሬዋን ፡ ትከለክል ፡ ዘንድ ፡ ማስቀ
ረት ፡ እንዳይቻላት ።
፴፩ የፀነስችም ፡ ሴት ፡ ምጥ ፡ በያዛት ፡ ጊዜ ፡ ማኅፀ
ኗን ፡ ዘግታ ፡ መከልከል ፡ እንዳይቻላት ፡ ሳትወ
ልድ ፡ ማምለጥ ፡ እንዳይቻላት ።
፴፪ ከእግዚአብሔር ፡ ታዞ ፡ ጠል ፡ ወደሷ ፡ ወርዷ
ልና ፡ ያንጊዜ ፡ በንድ ፡ ጊዜ ፡ ታስገኛቸዋለች ፡
እንጂ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ከሰማች ፡ በኋላ ፡
መቃብርም ፡ እንደዚሁ ፡ በሷ ፡ ዘንድ ፡ የተሰበ
ሰቡትን ፡ ሰዎች ፡ ከመነሣት ፡ መከልከል ፡ አት
ችልም ።
፴፫ ሥጋዎችም ፡ ሬሳቸው ፡ በወደቀበት ፡ ቦታ ፡ ይሰ
በሰባሉ ፡ ነፍሳት ፡ የሚኖሩባቸው ፡ ቦታቸውም ፡
ይከፈታሉ ፡ ነፍሳትም ፡ ቀድሞ ፡ ወደ ፡ ተለዩ
በት ፡ ወደ ፡ ሥጋ ፡ ይመለሳሉ ።
፴፬ ነጋሪትም ፡ በተመታ ፡ ጊዜ ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡
እንዳይን ፡ ጥቅሻ ፡ ፈጥነው ፡ ይነሣሉ ፡ ተነሥተ
ውም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ይቆማሉ ፡
እንደ ፡ እጃቸውም ፡ ሥራ ፡ ዋጋቸውን ፡ ይሰጣ
ቸዋል ።
የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ከሙታን ፡ ጋራ ፡ እንድትነሣ ፡ ፴፭
ታያለህ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ የሠራኸውንም ፡
ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ታደንቃለህ ፡ ኃጢአቶችህንም ፡
በፊትህ ፡ ተጽፈው ፡ በየሃቸው ፡ ጊዜ ፡ ያን ፡
ጊዜ ፡ የማይረባ ፡ ጸጸትን ፡ ትጸጸታለህ ።
ከሙታን ፡ ጋራ ፡ እንድትነሣ ፡ እንደ ፡ ሠራኸ ፴፮
ውም ፡ ሥራ ፡ ፍዳህን ፡ እንድትቀበል ፡ ታው
ቃለህ ።

ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

በበጎ ፡ ሥራቸው ፡ ዋጋቸውን ፡ ያገኙ ፡ ሰዎች ፡ ፩
ግን ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፡ የሞቱ ፡
ሰዎች ፡ አይነሡም ፡ እያሉ ፡ ቸል ፡ ያሉ ፡ ሰዎች ፡
ከማይጠቅም ፡ ክፉ ፡ ሥራቸው ፡ ጋራ ፡ የሞቱ ፡
ሰዎች ፡ እንደተነሡ ፡ በዩ ፡ ጊዜ ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡
ያዝናሉ ።
ያ ፡ የሠሩት ፡ ሥራቸው ፡ ይፈርድባቸዋል ፡ የሚ ፪
ከራከራቸውም ፡ ሳይኖር ፡ እንዲፈርድባቸው ፡
እነሳቸው ፡ ራሳቸው ፡ ያውቃሉ ።
ፍርድና ፡ ልቅሶ ፡ በሚደረግበት ፡ ቀን ፡ እግዚአ ፫
ብሔር ፡ በሚመጣበት ፡ ቀንና ፡ ቍርጥ ፡ ፍርድ ፡
በሚፈረድበት ፡ ቀን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡
የዘነጉ ፡ ሰዎች ፡ በሚቆሙት ፡ ቦታ ፡ ይቆማሉ ።
ፍጹም ፡ ጨለማ ፡ በሚሆንበት ፡ ቀን ፡ ጉምም ፡ ፬
በሚሳብበት ፡ ቀን ፡ ብልጭልጭታ ፡ በሚታይ
በት ፡ መብረቅ ፡ በሚሰማበት ፡ ቀን ።
መንቀጥቀጥና ፡ ፍርሃትም ፡ ዋዕይና ፡ ቀቅ ፡ ፭
ውርጭም ፡ በሚደረግበት ፡ ቀን ።
ክፉ ፡ ሥራ ፡ የሠራ ፡ ክፉ ፡ ሰው ፡ ፍዳ ፡ በሚቀ ፮
በልበት ፡ ቀን ፡ ንጹሕ ፡ ሰውም ፡ ንጹሕ ፡ ሥራ ፡
እንደሠራ ፡ ዋጋውን ፡ በሚቀበልበት ፡ ቀን ፡
ኃጢአተኛ ፡ ሰውም ፡ ኃጢአት ፡ እንደሠራ ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ የዘነጉ ፡ ሰዎች ፡ ፍዳ
ውን ፡ በሚቀበሉበት ፡ ቀን ፡ በሚቆሙበት ፡
ቦታ ፡ ይቆማሉ ።
ጌታ ፡ ከባርያው ፡ በማይከብርበት ፡ ቀን ፡ እመ ፯
ቤትም ፡ ከባርያዋ ፡ በማትከብርበት ፡ ጊዜ ።
ንጉሡም ፡ ከድኃ ፡ በማይከብርበት ፡ ጊዜ ፡ ሽማ ፰
ግሌም ፡ ከሕፃን ፡ በማይከብርበት ፡ ጊዜ ፡ አባት ፡
ከልጁ ፡ በማይከብርበት ፡ ጊዜ ፡ እናትም ፡ ከል
ጅዋ ፡ በማትከብርበት ፡ ጊዜ ።
ባለጸጋ ፡ ከድኃ ፡ በማይከብርበት ፡ ጊዜ ፡ ትቢ ፱
ተኛም ፡ ከተዋረደ ፡ ሰው ፡ በማይከብርበት ፡
ጊዜ ፡ ታላቁም ፡ ከታናሹ ፡ በማይከብርበት ፡
ጊዜ ፡ ፍርድ ፡ የሚፈርድበት ፡ ቀን ፡ ናትና ፡
መቻያና ፡ ፍዳ ፡ የሚቀበሉበት ፡ ቀን ፡ ናትና ፡
ሁሉም ፡ ኃጢአት ፡ እንደሠራ ፡ ፍዳ ፡ የሚቀበ
ልበት ፡ ቀን ፡ ናትና ።
በጎ ፡ ሥራም ፡ የሠሩ ፡ ሰዎች ፡ ዋጋቸውን ፡ የሚ ፲
ቀበሉበት ፡ ቀን ፡ ናትና ፡ ኃጢአት ፡ የሠሩ ፡ ሰዎ
ችም ፡ ፍዳቸውን ፡ የሚቀበሉበት ፡ ቀን ፡ ናትና ።
ዋጋቸውን ፡ ያገኙም ፡ ሰዎች ፡ ደስ ፡ የሚሰኙ ፲፩

ብት ፡ ቀን ፡ ናትና ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡
የዘነጉ ፡ ሰዎች ፡ በሚቆሙበት ፡ በታ ፡ ይቆማሉ ።
የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ አይነሡም ፡ እያሉ ፡ መጻሕፍ
ትን ፡ የሚያሳብሉ ፡ አስተኞች ፡ የሚያደርጉ ፡
ሰዎች ፡ ትንሣኤን ፡ ያያሉ ።
፲፪ በዚህ ፡ ዓለም ፡ በጎ ፡ ሥራን ፡ ያልሠሩ ፡ የዚህ ፡
ዓለም ፡ ኃጢአተኞች ፡ መረጋጋት ፡ የሌለው ፡
ኀዘን ፡ ስላገኛቸው ፡ በሠሩት ፡ ኃጢአታቸው ፡
ያን ፡ ጊዜ ፡ ያለቅሳሉ ።
፲፫ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሳሉ ፡ በጎ ፡ ሥራን ፡ ሠርተዋ
ልና ፡ እንደዚሁም ፡ ሁሉ ፡ በጎ ፡ ሥራን ፡ የሠሩ ፡
የደጋግ ፡ ሰዎች ፡ ተድላ ፡ ደስታቸው ፡ እስከ ፡
ዘላለም ፡ ድረስ ፡ አይፈጸምም ።
፲፬ ከሞቱ ፡ በኋላ ፡ እንዲነሡ ፡ አውቀዋልና ፡ ከፈጣ
ሪያቸውም ፡ ሕግ ፡ አልወጡም ።
፲፭ ከሕጉ ፡ ስላልወጡ ፡ ሁለት ፡ ድኅነት ፡ ይወርሳሉ ፡
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ዘራቸውን ፡ አበዛ ፡ ልጆቻቸው
ንም ፡ አከበረ ።
፲፮ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ በሚነሡበት ፡ ጊዜ ፡ በለጸጎችም ፡
በሚደኸዩበት ፡ ጊዜ ፡ ላበቶቻቸው ፡ የማለላ
ቸው ፡ ድኅነት ፡ የሚገኝበት ፡ መንግሥት ፡ ሰማ
ያትን ፡ አወረሳቸው ።
፲፯ ኃጢአትን ፡ የሠሩ ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ መነሣትን ፡
የማያምኑ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ የማይጠ
ብቁ ፡ የመነሣትንም ፡ ቀን ፡ የማያስቡ ፡ ሰዎች ፡
ያለቅሳሉ ።
፲፰ መጨረሻ ፡ የሌላት ፡ መረጋጋትና ፡ ድኅነትም ፡
የሌለበት ፡ የምታገኛቸውንም ፡ መከራ ፡ ያን ፡
ጊዜ ፡ ያያሉ ፡ በልቡናቸውም ፡ ዕረፍትና ፡ መረ
ጋጋት ፡ የሌለው ፡ ኀዘን ፡ አለው ።
፲፱ የማይጠፋ ፡ እሳትና ፡ የማያንቀላፋ ፡ ትልም ፡
ያገኛቸዋል ።
፳ ሥጋቸውም ፡ ባለበት ፡ በታ ፡ እሳት ፡ ድኝ ፡
ጥቅል ፡ ነፋስ ፡ ውርጭ ፡ በረድ ፡ ቀቅ ፡ አለ ፡
ይህ ፡ ሁሉ ፡ በላያቸው ፡ ይዘንማል ።
፳፩ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ መነሣትን ፡ ለማያምኑ ፡ ሰዎች ፡
ገሃነመ ፡ እሳት ፡ አለባቸው ።

ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

፩ በቈረጥክቸው ፡ ጊዜ ፡ ፈጥነው ፡ ይወጣሉና ፡
በሥጋህ ፡ በእግርህና ፡ በእጅህ ፡ ጥፍር ፡ በራስ
ህም ፡ ጠጉር ፡ ያለውን ፡ እስኪ ፡ አንተ ፡ አስ
በው ፡ ልቡና ፡ እንዳለህ ፡ ሃይማኖትና ፡ ዕውቀ
ትም ፡ እንዳለህ ፡ በዚህ ፡ ትንሣኤን ፡ ዕወቅ ።
፪ የእግርህና ፡ የእጅህ ፡ ጥፍር ፡ የራስህም ፡ ጸጉር ፡
እሊህ ፡ ከወዴት ፡ ይወጣሉ ፡ ትላለህ ፡ ከሞትህ ፡
በኋላ ፡ እንድትነሣ ፡ አንተ ፡ ታውቅ ፡ ዘንድ ፡
በሌላ ፡ ሥጋ ፡ ያይደለ ፡ ባንተ ፡ ሥጋ ፡ የሚደ
ረግ ፡ መነሣትን ፡ እንድታውቅ ፡ ይወጡ ፡ ዘንድ ፡
እግዚአብሔር ፡ ያዘጋጀው ፡ አይደለምን ።
፫ ትንሣኤ ፡ ሙታን ፡ የለም ፡ እያልህ ፡ ሰዎችን ፡
ስላሳትህ ፡ ኃጢአትና ፡ በደልን ፡ እንደ ፡ ሠራህ ፡
ሙታን ፡ በሚነሡበት ፡ ጊዜ ፡ አንተ ፡ ፍዳህን ፡
ትቀበላለህ ።

አሁንም ፡ ስንዴም ፡ ቢሆን ፡ ገብስም ፡ ቢሆን ፡ ፬
አንተ ፡ ስንኳ ፡ የዘራኸው ፡ ይበቅል ፡ ዘንድ ፡
እምቢ ፡ ብሎ ፡ አይቀርምና ፡ ፍዳህን ፡ የምትቀ
በልበት ፡ ቀን ፡ በደረሰች ፡ ጊዜ ፡ ታያታለህ ።
ዳግመኛም ፡ አንተ ፡ የተከልከው ፡ ተክል ፡ አል ፭
በቀልም ፡ አይልም ፡ የበለስ ፡ እንጨትና ፡ የወ
ይን ፡ ሐረግም ፡ ቢሆን ፡ ፍሬውና ፡ ቅጠሉ ፡
አይለወጥም ።
ወይን ፡ ብትተክል ፡ በለስ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ አይ ፮
ለወጥም ፡ በለስም ፡ ብትተክል ፡ ወይን ፡ ይሆን ፡
ዘንድ ፡ አይለወጥም ፡ ስንዴም ፡ ብትዘራ ፡ ገብስ ፡
ይሆን ዘንድ ፡ አይለወጥም ።
ሁሉ ፡ በየዘሩ ፡ በየወገኑ ፡ በየፍሬው ፡ በየእን ፯
ጨቱ ፡ በየቅጠሉ ፡ በየሥሩ ፡ ከእግዚአብሔር ፡
በተገኘ ፡ ይቅርታ ፡ ጠል ፡ በረከትን ፡ ተቀብሎ ፡
ፍሬን ፡ ያወጣል ፡ እንጂ ፡ ገብስም ፡ ብትዘራ ፡
ስንዴ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ አይለወጥም ።
እንደዚሁ ፡ ሁሉ ፡ መቃብርም ፡ ሥጋና ፡ ነፍስን ፡ ፰
ታስገኝ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ዘራ
ባት ፡ ሰዎችን ፡ ታስገኛለች ፡ እግዚአብሔር ፡
የዘራቸው ፡ ሥጋና ፡ ነፍስ ፡ ተዋሕደው ፡ ይነ
ሣሉ ፡ እንጂ ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ የሠሩ ፡ ሰዎች ፡ ክፉ ፡
ሥራ ፡ በሠሩ ፡ ሰዎች ፡ አይለወጡም ፡ ክፉ ፡
ሥራም ፡ የሠሩ ፡ ሰዎች ፡ በጎ ፡ ሥራም ፡ በሠሩ ፡
ሰዎች ፡ አይለወጡም ።
ነጋሪት ፡ የሚመታበት ፡ ሰዓት ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ ፱
የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ ከእግዚአብሔር ፡ በሚገኝ ፡ በይ
ቅርታው ፡ ጠል ፡ ይነሣሉ ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ የሠሩ ፡
ሰዎች ፡ የሕይወት ፡ ትንሣኤን ፡ ይነሣሉ ፡ ዋጋቸ
ውም ፡ እግዚአብሔር ለደጋጎች ፡ ሰዎች ፡ ያዘ
ጋጀው ፡ መከራና ፡ ደዌ ፡ የሌለበት ፡ ከዚህ ፡
በኋላ ፡ ዳግመኛም ፡ የማይሞቱበት ፡ የንጹሐን ፡
ማደሪያ ፡ የሚሆን ፡ ተድላ ደስታ ፡ ያለበት ፡
ገነት ፡ ነው ።
ክፉ ፡ ሥራ ፡ የሠሩ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ የቍርጥ ፡ ፲
ፍርድ ፡ መነሣትን ፡ ተነሥተው ፡ ከሳታቸው ፡
ከዲያብሎስ ፡ ጋራ ።
ክፉዎች ፡ ከሆኑ ፡ ከአዳም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ፲፩
እንድ ፡ ሰው ፡ ስንኳ ፡ ይድን ፡ ዘንድ ፡ ከማይወዱ ፡
ከሠራዊቶቹ ፡ ከአጋንንትም ፡ ጋራ ።
የጨለማ ፡ ዳርቻ ፡ ወደ ፡ ሆነ ፡ ጥርስ ፡ ማፋጨ ፲፪
ትና ፡ ልቅሶ ፡ ወዳለበት ፡ ቸርነትና ፡ ይቅርታ ፡
ወደሌለበት ፡ እስከ ፡ ዘላለምም ፡ ድረስ ፡ መውጫ ፡
ወደሌለበት ፡ ለዘላለሙ ፡ ከሲኦል ፡ በታች ፡
ወዳለ ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡ ይወርዳሉ ። በሥጋቸው ፡
ሳሉ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ በሕይወታቸው ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡
አልሠሩምና ።
ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ሥጋና ፡ ነፍስ ፡ ተዋሕደው ፡ ፲፫
በሚነሡበት ፡ ጊዜ ፡ ይፈረድባቸዋል ።
እግዚአብሔር ፡ የተአምራቱን ፡ ብዛት ፡ አንድ ፲፬
ነት ፡ የሚያሳይበት ፡ የሥጋና ፡ የነፍስን ፡ መነ
ሣት ፡ ለማያምኑ ፡ ሰዎች ፡ ወዮላቸው ።
ሁሉም ፡ እንዱም ፡ እንዱም ፡ እንደ ፡ ሥራው ፡ ፲፭
እንደ ፡ እጁም ፡ ድካም ፡ ዋጋውን ፡ ይቀበላል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፯ ፡

፩ የስንዴ ፡ ቅንጣት ፡ ካልፈረሰች ፡ አትበቅልም ፡
አታፈራም ፡ የስንዴ ፡ ቅንጣት ፡ ብትፈርስ ፡
ግን ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ሥር ፡ ትሰዳለች ፡ ቅጠል ፡
ታወጣለች ፡ ዝርዝር ፡ ይሆናል ፡ ያፈራል ፡፡
፪ አንዲቱ ፡ የስንዴ ፡ ቅንጣት ፡ ብዙ ፡ ቅንጣት ፡
እንድትሆን ፡ እናንተ ፡ ታውቃላችሁ ፡፡
፫ እንደዚሁም ፡ ሁሉ ፡ ይህች ፡ ቅንጣት ፡ ከውኃና ፡
ከነፋስ ፡ ከመሬትም ፡ ጠል ፡ ተነሥታ ፡ ትበቅላ
ለች ፡ ስንዴ ፡ ያለ ፡ ፀሐይ ፡ ፍሬ ፡ ማፍራት ፡
አይችልምና ፡ ፀሐይ ፡ ግን ፡ ስለ ፡ እሳት ፡ ፈንታ ፡
ነው ፡፡
፬ ነፋስም ፡ ስለ ፡ ነፍስ ፡ ፈንታ ፡ ነው ፡ ያለ ፡ ነፋ
ስም ፡ ስንዴ ፡ ማፍራት ፡ አይችልም ፡ ውኃ
ውም ፡ ምድርን ፡ ያጠጣታል ፡ ያጠግባታል ፡፡
፭ አመድ ፡ የምትሆን ፡ መሬትም ፡ ውኃን ፡ ከጠ
ጣች ፡ በኋላ ፡ ሥርን ፡ ታስገኛለች ፡ ጫፏም ፡
ወደላይ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ይላል ፡ እግዚአብሔር ፡
የባረከትን ፡ ያህል ፡ ታፈራለች ፡፡
፮ የስንዴ ፡ ቅንጣት ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ የፈጠ
ራት ፡ ነባቢት ፡ ነፍስ ፡ ያደረችበት ፡ የአዳም ፡
አምሳል ፡ ነው ፡ የወይን ፡ እንጨትም ፡ እንደ
ዚሁ ፡ ውኃን ፡ ይጠጣል ፡ ሥርም ፡ ይሰዳል ፡
የቀጠነ ፡ የሥር ፡ ወገንም ፡ ውኃን ፡ ይጠጣል ፡፡
፯ ከእግዚአብሔር ፡ የተገኘ ፡ የይቅርታ ፡ ጠል ፡
ረጃጅም ፡ የሆኑ ፡ የአረጎችን ፡ ጫፎች ፡ ያጠጣ
ቸዋልና ፡ ውሀይቱንም ፡ ወደ ፡ ቅጠሉ ፡ ጫፎች ፡
ወደ ፡ ላይ ፡ ያወጣታል ፡ በፀሐይ ፡ ሙቀት ፡
ይዘረዝራል ፡ በእግዚአብሔርም ፡ ፈቃድ ፡ ፍሬ ፡
ያፈራል ፡፡
፰ ልቡናን ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ በጎ ፡ መዓዛን ፡ ይሆ
ናል ፡ በበሉትም ፡ ጊዜ ፡ እንደማያሰጠማ ፡
ውሀና ፡ እንደማያስርብ ፡ እህል ፡ ያጠግባል ፡ በጠ
መቁትም ፡ ጊዜ ፡ የዘላለው ፡ ደም ፡ ይሆናል ፡፡
፱ ወይን ፡ የሰው ፡ ልቡናን ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ፡ ብሎ ፡
በመዝሙር ፡ እንደ ፡ ተነገረ ፡ በጠጡትም ፡ ጊዜ ፡
የሰው ፡ ልብ ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ፡ ፊታ ፡ ፊታ ፡ ያለ ፡
ሰውም ፡ አፉን ፡ ከፍቶ ፡ በጠጣ ፡ ጊዜ ፡ ይሰክ
ራል ፡ ይጠጣል ፡ በሰምበውም ፡ ይመላል ፡
ደሙም ፡ ወደ ፡ ልቡ ፡ ይፈሳል ፡፡
፲ የወይን ፡ ስክር ፡ ፈጽሞ ፡ ያስታልና ፡ አእምሮ
ውን ፡ ያሳጣዋልና ፡ ጕዳጕዱንና ፡ ገደሉን ፡
እንደ ፡ ሰፊ ፡ ሜዳ ፡ ያደርገዋል ፡ በእግሩና ፡
በእጁ ፡ ያለ ፡ እንቅፋትና ፡ እሾህም ፡ አያው
ቅም ፡፡
፲፩ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ መነሣትን ፡ በሚያምኑና ፡ ፈቃ
ዱን ፡ በሚያደርጉ ፡ ሰዎች ፡ ስሙ ፡ ይመሰገን ፡
ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ በፍሬዋና ፡ በወይን ፡
እንጨት ፡ እንዲህ ፡ አደረገ ፡፡
፲፪ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ መነሣትን ፡ የሚያምኑ ፡ ሰዎችን ፡
በመንግሥት ፡ ሰማያት ፡ ደስ ፡ ያሰኛቸዋል ፡፡

## ምዕራፍ ፡ ፲፰ ፡

የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ መነሣትን ፡ የማታምኑ ፡ ፩
ሰዎች ፡ ምን ፡ ያህል ፡ ስተትን ፡ ትስታላችሁ ፡
ወደማታውቁትም ፡ ቦታ ፡ በወሰዷችሁ ፡ ጊዜ ፡
የማይረባ ፡ ጸጸትን ፡ ትጸጸታላችሁ ፡ የሞቱም ፡
ሰዎች ፡ በነፍስና ፡ በሥጋ ፡ ተዋሕደው ፡ የሚነ
ሡትን ፡ መነሣት ፡ ስለ ፡ አላመናችሁ ፡ ሰዎች ፡
ወደ ፡ ገሃነምም ፡ በጣሏችሁ ፡ ጊዜ ፡፡
ትቢያ ፡ አመድ ፡ የሆኑ ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ እንዳ ፪
ይነሡ ፡ እናውቃለን ፡ እያላችሁ ፡ የባልንጀሮቻ
ቸውን ፡ ልቡና ፡ አስታችኋልና ፡ በጎውንም ፡
ክፉውንም ፡ ብትሠሩ ፡ እንደሥራችሁ ፡ ዋጋች
ሁን ፡ ትቀበላላችሁ ፡፡
ለሞታቸው ፡ ዕረፍት ፡ የለውምና ፡ ለሚመጣበ ፫
ቸው ፡ መቅሠፍታቸውም ፡ ኃይል ፡ የላቸው
ምና ፡ በመከራቸውም ፡ የፀኑ ፡ አልሆኑምና ፡
ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ባልንጀሮቻቸውን ፡ ያስታሉ ፡
በእግዚአብሔር ፡ አደባባይ ፡ ይቆሙ ፡ ዘንድ ፡
አላቸውና ፡፡
በመዓቱ ፡ በተቈጣቸው ፡ ጊዜ ፡ ፈጽመው ፡ ይፈ ፬
ራሉ ፡ ከለመኖር ፡ ወደ ፡ መኖር ፡ መጥተው ፡ እን
ደተፈጠሩ ፡ ስለ ፡ አላወቁ ፡ ሳያውቁ ፡ የእግዚአ
ብሔርን ፡ ሕግ ፡ ይናገራሉና ፡ ክፉ ፡ ስለ ፡ ሠሩ ፡
ሁሉ ፡ ይፈረድባቸዋል ፡፡
የሚሄዱበት ፡ ገሃነምን ፡ አያውቁም ፡ ቍጡ ፭
ዎች ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፡ በሥራቸውም ፡ ጠማሞች ፡
ስለ ፡ ሆኑ ፡ እንደ ፡ ልቡናቸው ፡ ጥመት ፡ መጠን ፡
ለባልንጀራቸው ፡ ያስተምራሉና ፡ ትንሣኤ ፡
ሙታን ፡ የለም ፡ እያሉ ፡ ጠማማ ፡ ነገርን ፡ የሚ
ያስተምሩ ፡ ክፉዎችም ፡ ናቸውና ፡፡
የዚያን ፡ ጊዜ ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ እንዲነሡ ፡ ፮
ያውቃሉ ፡ ለአዳም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ የሚሆን ፡
የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ መነሣትን ፡ ስለ ፡ አላመኑ ፡ እን
ዲፈረድባቸውም ፡ ያውቃሉ ፡፡
ሁላችን ፡ የአዳም ፡ ልጆች ፡ ነንና ፡ ስለ ፡ አዳ ፯
ምም ፡ ሞተናልና ፡ ሁላችንንም ፡ ስለ ፡ አባታ
ችን ፡ ስለ ፡ አዳም ፡ ስሕተት ፡ ከእግዚአብሔር ፡
ዘንድ ፡ የሞት ፡ ፈርድ ፡ አግኝቶናልና ፡፡
ዳግመኛ ፡ በሠራነው ፡ ሥራችን ፡ ፍዳችንን ፡ ፰
እንቀበል ፡ ዘንድ ፡ ከዚያ ፡ ከባታችን ፡ ከአዳም ፡
ጋራ ፡ እንነሣለን ፡ በባታችን ፡ በአዳም ፡ በለማ
ወቅ ፡ ዓለም ፡ ለሞት ፡ ተገዝቷልና ፡፡
አዳም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ በመደፋ ፱
ፈሩ ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ፍዳን ፡ ተቀበልን ፡ በመ
ቃብር ፡ ሥጋችን እንደ ፡ ሰም ፡ ቀለጠች ፡ ሰው
ነቶቻችንም ፡ ጠፉ ፡፡
ምድርም ፡ ቅልጥማችንን ፡ ጠጣች ፡ ጠፋን ፡ ፲
ደም ፡ ግባታችንም ፡ በመቃብር ፡ ጠፋ ፡ ሥጋች
ንም ፡ በመቃብር ፡ ተቀበረ ፡ ያማረ ፡ ቃላችንም ፡
በመሬት ፡ ተቀበረ ፡፡
ከሚያበሩ ፡ ዓይኖቻችንም ፡ ትል ፡ ወጣ ፡ መል ፲፩

ካችንም ፡ በመቃብር ፡ ጠፉ ፡ ትቢያም ፡ ሆነ ።
፲፪፡ መልክ ፡ መልክም ፡ የነበሩ ፡ ቁመታቸው ፡ ያማረ ፡
የቃላቸውም ፡ ነገር ፡ የተከናወነ ፡ የጉልማሶች ፡
የመልክቸው ፡ ደም ፡ ግባት ፡ ወዴት ፡ አለ ፡ የአ
ርበኞችስ ፡ ጽናታቸው ፡ ወዴት ፡ አለ ።
፲፫፡ የነገሥታቱ ፡ ሠራዊታቸው ፡ የመኳንንቱስ ፡
ጌትነታቸው ፡ ወዴት ፡ አለ ፡ በፈረስ ፡ ማጌጥ ፡
በብርና ፡ በወርቅም ፡ ማጌጥ ፡ በሚያበራ ፡ መሣ
ርያም ፡ ማጌጥ ፡ ወዴት ፡ አለ ፡ አልጠፉምን ።
፲፬፡ የሚጣፍጥ ፡ የወይን ፡ መጠጥና ፡ የመብልስ ፡
ጣዕም ፡ ወዴት ፡ አለ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

፩፡ መኳንንቱንና ፡ ነገሥታቱን ፡ ባለጸጎችንና ፡
ሽማግሌችንም ፡ መልክ ፡ መልክሞች ፡ የሆኑ ፡
ሴቶችንም ፡ መልክ ፡ መልክም ፡ የሆኑ ፡ ቈነጃ
ጅትንም ፡ የሰበሰብሻቸው ፡ ምድር ፡ ሆይ ፡ ክንች ፡
የተነሣ ፡ ወዮ ።
፪፡ አርበኞች ፡ የሆኑ ፡ ደም ፡ ግባት ፡ ያላቸው ፡
ባተ ፡ መልክምም ፡ የሆኑ ፡ ልቡናና ፡ ዕውቀ
ትም ፡ ያላቸው ፡ ቃላቸውም ፡ እንደምታንጐራ
ጕር ፡ በገና ፡ እንደ ፡ ክራርና ፡ እንደ ፡ መሰን
ቆም ፡ አመታት ፡ ያማረ ፡ የሆነ ፡ ቃል ፡ ያላቸው ።
፫፡ የወይን ፡ መጠጥ ፡ ደስ ፡ እንዲያሰኝ ፡ ደስ ፡ የሚያ
ሰኝ ፡ ዜማም ፡ ያላቸው ፡ ዓይኖቻቸውም ፡ እንደ ፡
አጥቢያ ፡ ኮከብ ፡ የሚያበሩ ።
፬፡ ቀኝ ፡ እጃቸውም ፡ የሚሰጥና ፡ የሚነሣ ፡ እንደ
ሚያነሣና ፡ እንደሚሆኑ ፡ ጽኑዕ ፡ የሆነ ፡ የሚን
ድፉ ፡ እግሮቻቸውም ፡ ለማየት ፡ ያማሩ ፡ የሆኑ ፡
እንደሚፋጠኑ ፡ መንኰራኩሮችም ፡ የሚሮጡ ፡
ሰዎችን ፡ የሰበሰብሻቸው ፡ ምድር ፡ ሆይ ፡ ክንች ፡
የተነሣ ፡ ወዮ ።
፭፡ በእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ ተልከሃልና ፡ የመ
ልክ ፡ የመልክም ፡ ሰዎችን ፡ ነፍሳት ፡ ከሥጋ
ቸው ፡ የለየህ ፡ ሞት ፡ ሆይ ፡ ክንተ ፡ የተነሣ ፡
ወዮ ።
፮፡ እግዚአብሔር ፡ ክንቺ ፡ ያስገኛቸውን ፡ ወዳን
ችም ፡ የመለሳቸውን ፡ ብዙ ፡ ሰዎችን ፡ ሰብስበ
ሻልና ፡ አንቺ ፡ ምድር ፡ ክንቺ ፡ የተነሣ ፡ ወዮ ፡
ክንቺ ፡ ተገኘን ፡ በፈቃደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወዳ
ንች ፡ ተመለስን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡
በላይሽ ፡ ደስ ፡ አለን ።
፯፡ ለሬሳችን ፡ ምንጣፍ ፡ ሆንሽ ፡ በላይሽ ፡ ተመ
ላለስን ፡ በውስጥሽም ፡ ተቀብርን ፡ ፍሬሽን ፡
በላን ፡ አንቺም ፡ ሥጋችንን ፡ በላሽ ።
፰፡ ከምንጭሽም ፡ የተገኘውን ፡ ውኃ ፡ ጠጣን ፡
አንቺም ፡ የደማችንን ፡ ምንጭ ፡ ጠጣሽ ፡ ከም
ድርነትሽ ፡ የተገኘውን ፡ ፍሬ ፡ በላን ፡ አንቺም ፡
የሰውነታችን ፡ ሥጋ ፡ በላሽ ።
፱፡ ምግባችንን ፡ ልትሆኚ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘ
ዘሽ ፡ ያማረ ፡ ጠል ፡ ከሰው ፡ ከመሬትነትሽ ፡
እህልን ፡ በላን ፡ አንቺም ፡ የሥጋችንን ፡ ደም ፡
ግባት ፡ ተቀብለሽ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘሽ ፡
ለምግብሽ ፡ ትቢያን ፡ አደረግሽው ።

ኃይለኞች ፡ የሆኑ ፡ መኳንንቱንና ፡ ነገሥታ ፲፡
ቱን ፡ የሰበሰብህ ፡ ሞት ፡ ሆይ ፡ ክንተ ፡ የተነሣ ፡
ወዮ ፡ የፈጠራቸው ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘ
ዘህ ፡ ከገናንነታቸው ፡ ከማስፈራታቸው ፡ የተ
ነሣ ፡ አልፈራህም ፡ ሞት ፡ ሆይ ፡ ክንተ ፡ የተነሣ ፡
ወዮ ፡ ጠም ፡ አዳሪውንም ፡ አልናቅህም ።
መልክቸውም ፡ ላማረ ፡ ሰዎች ፡ አልራራህም ፡ ኃይ ፲፩፡
ለኞችንና ፡ አርበኞችንም ፡ አልተውህም ፡ ድሆ
ችንና ፡ ባለጸጎችን ፡ ደጋጎችንና ፡ ክፉዎችንም ፡
ልጆችና ፡ ሽማግሎችንም ፡ ሴቶችንና ፡ ወን
ዶችንም ፡ አልተውህም ።
በጎ ፡ ነገርን ፡ የሚያስቡ ፡ ከሕጉም ፡ ያልወጡ ፡ ፲፪፡
ሰዎችን ፡ አልተውህም ፡ በሥራቸውም ፡ እንደ ፡
እንስሳ ፡ የሆኑ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ የሚያስቡትን ፡
በመልክቸው ፡ ደም ፡ ግባት ፡ በነገራቸው ፡ ጣዕ
ምና ፡ በቃላቸው ፡ ፈጽመው ፡ ያማሩትን ፡
አልተውህም ፡ ሞት ፡ ሆይ ፡ ክንተ ፡ የተነሣ ፡
ወዮ ።
ቃላቸው ፡ ቀጡ ፡ የሆነ ፡ አፉቸውም ፡ እርግማ ፲፫፡
ንን ፡ የተመላ ፡ ሰዎችን ፡ አልተውህም ፡ በጨ
ለማና ፡ በብርሃን ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎችን ፡ ነፍሶቻ
ቸውንም ፡ በቦታዎችህ ፡ ሰበሰብህ ፡ ሞት ፡ ሆይ ፡
ክንተ ፡ የተነሣ ፡ ወዮ ።
ምድርም ፡ ነጋሪት ፡ እስኪመታ ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ ፲፬፡
እስኪነሡ ፡ ድረስ ፡ በዋሻም ፡ በመሬትም ፡ የሚ
ኖሩትን ፡ ሰዎች ፡ ሥጋቸውን ፡ ሰበሰበች ።
በእግዚአብሔር ፡ ትእዛዝና ፡ በነጋሪት ፡ መመ ፲፭፡
ታት ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ እንደ ፡ ዓይን ፡ ጥቅሻ ፡
ፈጥነው ፡ ይነሣሉና ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ የሠሩ ፡ ሰዎች ፡
በሠሩት ፡ ኃጢአታቸው ፡ ብዛት ፡ መጠን ፡ ፍዳ
ቸውን ፡ ይቀበላሉ ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ የሠሩ ፡ ሰዎ
ችም ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።

## ምዕራፍ ፡ ፳ ።

ፈርተን ፡ ተንቀጥቅጠን ፡ በፊቱ ፡ በቆምን ፡ ፩፡
ጊዜ ፡ በዚህም ፡ ዓለም ፡ የሠራነው ፡ ሥራችን ፡
ሁሉ ፡ እንዳይቀር ፡ እንዳይሠወር ፡ እመኑኝ ።
ለጕዳናችንም ፡ ስንቅ ፡ ባልያዝን ፡ ጊዜ ፡ ለሰው ፪፡
ነታችንም ፡ ልብስ ፡ በሌለን ፡ ጊዜ ።
ለእጃችን ፡ ምርጕዝ ፡ ለእግራችንም ፡ ጫማ ፡ ፫፡
በሌለን ፡ ጊዜ ።
ድጥም ፡ ጐጣጐጥም ፡ ቢሆን ፡ ጨለማም ፡ ቢሆን ፡ ፬፡
እሾህም ፡ አሜከላም ፡ ቢሆን ፡ የውሆም ፡ ጥልቅ ፡
የጕድጓድም ፡ ጥልቅ ፡ ቢሆን ፡ አጋንንት ፡
እኛን ፡ የሚወስዱበትን ፡ ጎዳናውንም ፡ በማና
ውቅ ፡ ጊዜ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ የሠራነው ፡ ሥራ
ችን ፡ እንዳይቀር ፡ እንዳይሠወር ፡ እመኑኝ ።
የሚወስዱን ፡ አጋንንትን ፡ አናውቃቸውም ፡ ፭፡
ነገራቸውንም ፡ አንሰማም ።
እነሳቸው ፡ ጥቋቍሮች ፡ ናቸውና ፡ ወደ ፡ ጨለ ፮፡
ማም ፡ ይመሩናልና ፡ ፊታቸውን ፡ አናይም ።
ነፍሴ ፡ ከሥጋዬ ፡ በተለየች ፡ ጊዜ ፡ አቤቱ ፡ ፯፡
ጌታዬ ፡ ጎዳናየን ፡ አንተ ፡ ታውቀዋለህ ፡ በዚ
ያች ፡ በሐድኩባትም ፡ ጎዳና ፡ ወጥመድ ፡

ሠወሩ ፡ ወደቀኝም ፡ ተመልሼ ፡ አየሁ ፡ የሚያውቀኝ ፡ አጣሁ ፡ በዚያም ፡ የማመልጥበት ፡ የለኝ ፡ ብሎ ፡ ነቢዩ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ ወደ ፡ ጨለማም ፡ ይወስዱናልና ፡ ፊታቸውን ፡ አናይም ።
፰ አጋንንት ፡ እንዲዘበበቱበት ፡ ያውቃልና ፡ ወደ ማያውቀውም ፡ ጎዳና ፡ ይመሩታልና ፡ ይኸን ፡ መናገሩ ፡ ስለዚህ ፡ ነው ፡ ወደ ፡ ግራና ፡ ወደ ፡ ቀኝም ፡ ቢመለስ ፡ የሚያውቀው ፡ ሰው ፡ የለም ።
፱ በአጋንንት ፡ መከከል ፡ ብቻውን ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ እሱንም ፡ የሚያውቀው ፡ የለም ።
፲ የጻድቃንን ፡ ነፍስ ፡ ይቀበሉ ፡ ዘንድ ፡ ድኅነት ፡ ወደሚገኝበት ፡ ወደ ፡ ብርሃን ፡ ቦታ ፡ ወደ ፡ ገነትም ፡ ይወስዱ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ደጋግ ፡ ሰዎች ፡ የሚላኩ ፡ ረቂቃን ፡ የሆኑ ፡ መላእክተ ፡ ብርሃን ፡ ናቸው ።
፲፩ ይቀበሏቸው ፡ ዘንድ ፡ በሠሩት ፡ ኃጢአታቸው ፡ ፍዳቸውን ፡ ሊቀበሉ ፡ ወደ ፡ ተዘጋጀላቸው ፡ ወደ ፡ ገሃነምም ፡ ይወስዷቸው ፡ ዘንድ ፡ የሚላኩ ፡ አጋንንትና ፡ መላእክተ ፡ ጽልመት ፡ ናቸው ።
፲፪ ወደ ፡ ጥፋት ፡ ለሚወስዷቸው ፡ ድኅነትና ፡ ዕረፍት ፡ ከገኛቸውም ፡ መከራ ፡ ማምለጥ ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ድረስ ፡ ከገሃነም ፡ መውጣት ፡ ለሌላቸው ፡ ለኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ ነፍሳት ፡ ወዮላቸው ።
፲፫ በቃየል ፡ ሥራ ፡ ጸንተው ፡ ኖረዋልና ፡ በበለዓምም ፡ በደል ፡ ዋጋ ፡ ጠፍተዋልና ፡ የሚያደርጉትም ፡ አጥተዋልና ፡ ለኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ ወዮላቸው ፡ ገንዘባቸው ፡ ያልሆነ ፡ የባዕድ ፡ ገንዘብን ፡ በግፍ ፡ ይወስዱ ፡ ዘንድ ፡ ወለድና ፡ እጅ ፡ መንሻን ፡ ለመቀበል ፡ ያመከኛሉና ።
፲፬ እነሳቸው ፡ በሠሩት ፡ ኃጢአታቸው ፡ በገሃነም ፡ ፍዳቸውን ፡ ይቀበላሉ ።

ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

፩ የጃቸው ፡ ሥራና ፡ ገንዘባቸው ፡ ያልሆነ ፡ የባዕድ ፡ ገንዘብን ፡ የሚሰበስቡ ፡ ሰዎች ፡ ወዬት ፡ አሉ ።
፪ ያለዋጋ ፡ የሰውን ፡ ገንዘብ ፡ ይወስዳሉና ፡ የምትደርስባቸው ፡ የሚሞቱበትንም ፡ ቀን ፡ ሳያውቁ ፡ ይሰበስባሉና ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ገንዘባቸውን ፡ ለባዕድ ፡ ይተዋሉ ።
፫ እንደ ፡ አባቶቻቸው ፡ እንደነሱ ፡ ያሉ ፡ ኃጥአንን ፡ በሥርቆሽም ፡ በቅሚያም ፡ ቢሆን ፡ አስጨንቀው ፡ የሚይዙ ፡ የኃጢአተኞች ፡ ወገኖቻቸውና ፡ ልጆቻቸውም ፡ ባባቶቻቸው ፡ ገንዘብ ፡ ደስ ፡ አይላቸውም ።
፬ በግፍ ፡ ሰብስበውላቸዋልና ፡ እንደ ፡ ጉም ፡ ሽንትም ፡ ነፋስ ፡ እንደሚበትነው ፡ ጢስም ፡ እንደሚረግፍ ፡ ሣርም ፡ ነውና ፡ ከእሳትም ፡ ፊት ፡ የተነካ ፡ እንደሚ | ልጥ ፡ ሰም ፡ የኃጥአን ፡ ክብራቸው ፡ እንደዚያ ፡ ይጠፋልና ፡ ያባቶቻቸው ፡ ገንዘብ ፡ የሚጠቅማቸው ፡ የለም ፡ ኃጥኡ ፡ ሰው ።
፭ እንደ ፡ ዋንዛ ፡ እንደ ፡ ዘግባ ፡ ኩብሮ ፡ ገኖ ፡ አየሁት ፡ በተመለስኩ ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ አጣሁት ፡ ፈለግሁ ፡ በቦታውንም ፡ አላገኘሁትም ፡ ብሎ ፡ ዳዊት ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ ያባቶቻቸው ፡ ገንዘብ ፡ የሚረባቸው ፡ የሚጠቅማቸው ፡ የለም ።
፮ የማይሞቱ ፡ መስሏቸው ፡ የሰውን ፡ ገንዘብ ፡ በግፍ ፡ ስለ ፡ ሰበሰቡ ፡ በልንጀሮቻቸውን ፡ የሚበድሉ ፡ ሰዎች ፡ እንዳይመኩ ፡ የኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ ጥፋታቸው ፡ እንደዚህ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ነው ።
፯ እናንተ ፡ ሰነፎች ፡ እንድትጠፉ ፡ ገንዘባችሁም ፡ ከናንተ ፡ ጋራ ፡ እንዲጠፋ ፡ አስቡ ፡ ብራችሁና ፡ ወርቃችሁም ፡ ቢበዛ ፡ የዛገ ፡ ይሆናል ።
፰ ብዙ ፡ ልጆችም ፡ ብትወልዱ ፡ ለብዙ ፡ መቃብር ፡ ይሆናሉ ፡ ብዙ ፡ ቤትንም ፡ ብትሠሩ ፡ የፈረሰ ፡ ይሆናል ።
፱ የፈጣሪያችሁ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ፈቃድ ፡ አልፈጸማችሁምና ፡ ከብትም ፡ ብታበዙ ፡ ለጠላቶቻችሁ ፡ ምርኮ ፡ ይሆናል ፡ ያልተባረከን ፡ ሆኗልና ፡ በጃችሁ ፡ የያዛችሁትም ፡ ገንዘብ ፡ ሁሉ ፡ አይገኝም ።
፲ በቤትም ፡ በዱርም ፡ ያለ ፡ ቢሆን ፡ በምድረ ፡ በዳና ፡ በመሰማርያ ፡ በታም ፡ ያለ ፡ ቢሆን ፡ በወይን ፡ አውድማና ፡ በእህል ፡ አውድማም ፡ ያለ ፡ ቢሆን ፡ አይገኝም ።
፲፩ የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ ስላልጠበቃችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከቤተ ፡ ሰብችሁ ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ ከመከራው ፡ አያድናችሁምና ፡ ከጠላቶቻችሁ ፡ ሁሉ ፡ የተነሣ ፡ ኀዘን ፡ ይሆንባችኋል ፡ እንጂ ፡ ከባሕርያችሁ ፡ በተወለደ ፡ ልጃችሁ ፡ ደስ ፡ አይላችሁም ።
፲፪ ሥራቱንና ፡ ሕጉን ፡ የጠበቁ ፡ ሰዎችን ፡ ግን ፡ ከበረከቱ ፡ አያስቸግራቸውም ፡ የለመኑትን ፡ ሁሉ ፡ ይሰጣቸዋል ፡ ከባሕርያቸው ፡ የተወለደ ፡ ልጃቸውንና ፡ የምድራቸውንም ፡ ፍሬ ፡ ይባርክላቸዋል ፡ እንጂ ።
፲፫ የሚገዙ ፡ እንዳይሆኑ ፡ ይገዙ ፡ ዘንድ ፡ በዙሪያቸው ፡ ባሉ ፡ በአሕዛብም ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ገዥ ፡ ያደርጋቸዋል ፡ በመሰምሪያቸውም ፡ በታ ፡ በረከቱን ፡ ሁሉ ፡ ይሰጣቸዋል ።
፲፬ በእጃቸው ፡ የያዙትን ፡ ሁሉ ፡ የርሻቸውን ፡ ፍሬ ፡ ሁሉ ፡ የከብቶቻቸውንም ፡ በታ ፡ ሁሉ ፡ ይባርክላቸዋል ፡ ከባሕርያቸው ፡ በተወለደ ፡ ልጃቸውም ፡ ደስ ፡ ያሰኛቸዋል ።
፲፭ ከብቶቻቸውንም ፡ አያሳንስባቸው ፡ ከመከራቸው ፡ ሁሉ ፡ ከድካምና ፡ ከበሽታም ፡ ከጥፋትም ፡ ከማያውቁትና ፡ ከሚያውቁት ፡ ጠላታቸው ፡ ያድናቸዋል ።
፲፮ በፍርድም ፡ ጊዜ ፡ ይከራከርላቸዋል ፡ ከክፉ ፡ ነገርና ፡ ከመከራም ፡ ከሚከራከራቸውም ፡ ሁሉ ፡ ያድናቸዋል ፡ በመጀመሪያው ፡ ዘመን ፡ የድንኳኑን ፡ ሥራ ፡ የሚሠራ ፡ ሕጉን ፡ የሚጠብቅ ፡ የድንኳኑንም ፡ ሥራት ፡ የሚጠብቅ ፡ በእግዚአብሔርም ፡ ፈቃድ ፡ ጸንቶ ፡ የሚኖር ፡ ካህን ፡ ቢኖር ፡ በመጀመርያ ፡ ሥራት ፡ በሕጉም ፡ ሁሉ ፡ አሥራቱን ፡ ከሰው ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ከብት ፡

ድረስ ፡ መጀመርያ ፡ የተወለደውን ፡ ይሰጡት ፡
ነበርና ፡ ከመከራው ፡ ሁሉ ፡ ያድናቸው ፡ ነበር ።
፲፯፡ ሙሴ ፡ የነዌ ፡ ልጅ ፡ ኢያሱን ፡ እንዳዘዘው ፡
በኀራቸው ፡ ሁሉ ፡ ሀገረ ፡ ምስክይ ፡ ነበር ፡ በሚ
ፈርዱበት ፡ ለሚፈርዱለት ፡ ፍርድን ፡ እስኪፈ
ርዱ ፡ ድረስ ፡ በለማወቅ ፡ በማወቅም ።
፲፰፡ ነፍስ ፡ የገደለ ፡ ሰው ፡ ቢኖር ፡ ይድን ፡ ዘንድ ፡
በዚያ ፡ ይማጠን ፡ ነበር ።
፲፱፡ ቀድሞ ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ ጠብ ፡ እንዳለው ፡ በልቡ
ናችሁ ፡ መርምሩ ፡ አላቸው ፡ ምሳርም ፡ ቢሆን ፡
ደንጊያም ፡ ቢሆን ፡ እንጨትም ፡ ቢሆን ፡ ባለማ
ወቅ ፡ ከእጁ ፡ ወድቋልና ፡ ያ ፡ የወደቀበት ፡ ሰው ፡
ሞተብኝ ፡ ቢል ፡ መርምራችሁ ፡ አድኑት ፡ ባለ
ማወቅ ፡ ከደረገው ፡ ይዳን ።
፳፡ አውቆ ፡ ቢያደርገው ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ኃጢአቱ ፡
ፍዳውን ፡ ይቀበላል ፡ የሚምረውም ፡ የለ ፤ ባለ
ማወቅ ፡ ቢገድለው ፡ ግን ፡ በለማወቅ ፡ አድርጎታ
ልና ፡ እንዳይሞት ፡ መርምራችሁ ፡ አድኑት ።
፳፩፡ ከኃጢአቱ ፡ ሁሉ ፡ ይርቁ ፡ ዘንድ ፡ ሥራላቸው ፡
እንጂ ፡ ከእግዚብአሔር ፡ ሕግ ፡ እንዳይወጡ ፡
ሙሴ ፡ ለእስራኤል ፡ ልጆች ፡ እንደዚህ ፡ ሠርቶ
ላቸው ፡ ነበር ።
፳፪፡ በፍርዱና ፡ በእውነተኛ ፡ ሕጉ ፡ ፀንተው ፡ ይኖሩ ፡
ዘንድ ፡ ጣዖት ፡ ከማምለክ ፡ ሙቶ ፡ ያደረውንና ፡
ሰይፍ ፡ ንሮ ፡ የቆረጠውን ፡ ከመብላት ፡ በእግዚ
አብሔር ፡ ትእዛዝ ፡ ፀንተው ፡ የሚኖሩ ፡ እንደ
ሥራላቸውም ፡ ከክፉ ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ የሚርቁ ፡
የአዳም ፡ ልጆች ፡ ይሠሩት ፡ ዘንድ ፡ ከማይገባ
ውም ፡ ሁሉ ፡ ፈጽመው ፡ ይርቁ ፡ ዘንድ ፡ አዘዛ
ቸው ።
፳፫፡ ሰውነታቸውን ፡ ያድኑ ፡ ዘንድ ፡ ብን ፡ ከሠሩ ፡
ከበቶቻቸውም ፡ ጋራ ፡ ማደሪያቸውን ፡ ያገኙ ፡
ዘንድ ፡ በሰማይ ፡ ባሉት ፡ ድንኳን ፡ አምሳል ፡
ከሥራላቸው ፡ ትእዛዝ ፡ እንዳይወጡ ፡ አዘዛ
ቸው ።
የእግዚአብሔርን ፡ ፈቃድ ፡ ከደረጉ ፡ ከሴትና ፡ ፳፬፡
ከአዳም ፡ ተወልደዋልና ፡ በእግዚአብሔር ፡
ቃል ፡ ያመኑ ፡ በትእዛዙም ፡ ፀንተው ፡ የኖሩ ፡
ሰዎች ፡ እነሳቸው ፡ የደጋግ ፡ ሰዎች ፡ ልጆች ፡
ይባላሉ ።
የአዳም ፡ ልጆች ፡ ነንና ፡ በጎ ፡ ሥራን ፡ እግዚአ ፳፭፡
ብሔርን ፡ ደስ ፡ የሚያሰኘውን ፡ ሁሉ ፡ እንሥራ ፡
ዘንድ ፡ በሱ ፡ አምሳል ፡ በሱ ፡ መልክ ፡ ፈጥሮና
ልና ፡ አይንቀውም ።
ወዳጆቹን ፡ ፈጽሞ ፡ አይለይምና ፡ በጎ ፡ ሥራን ፡ ፳፮፡
ብንሠራ ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ ከሠሩ ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡
ድኅነት ፡ ያለበት ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያትን ፡ እን
ወርሳታለን ።
በንጹሕ ፡ የሚለምኑትን ፡ ሰዎች ፡ ፈጽሞ ፡ ይወ ፳፯፡
ዳቸዋል ፡ ጸሎታቸውንም ፡ ይሰማቸዋል ፡ ጨክ
ነውም ፡ ንስሐ ፡ የሚገቡትን ፡ ሰዎች ፡ ንስሐቸ
ውን ፡ ይቀበላቸዋል ፡ ሥራቱንና ፡ ሕጉን ፡ ትእ
ዛዙንም ፡ ለሚጠብቁ ፡ ሰዎች ፡ ጽናትና ፡ ኃይ
ልን ፡ ይሰጣቸዋል ።
ፈቃዱን ፡ ያደረጉ ፡ ሰዎች ፡ ለዘላለሙ ፡ በመን ፳፰፡
ግሥቱ ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፡ የቀደ
ሙም ፡ በኋላ ፡ የተነሡ ፡ ሰዎችም ፡ ቢሆኑ ፡
ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዘላለሙ ፡ ድረስ ፡ ምስ
ጋና ፡ ያቀርቡለታል ።
ለዘላለሙ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ክብር ፡ ይግባ
ውና ፡ ሁለተኛው ፡ መቃብያን ፡ ደረሰ ፡ ተፈ
ጸመ ።





# መጽሐፈ ፡ መቃብያን ፡ ሣልስ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ ቸር ፡ የዋህ ፡ የሆነ ፡ የበደለ ፡ ሰውንም ፡
ያሳት ፡ የፈጣሪውንም ፡ ሥራ ፡ የሚጠላት ፡ ዲያ
ብሎስን ፡ ተበቅሎ ፡ የሚያጠፋ ፡ በኋላ ፡ ዘመን ፡
ወደነሳቸው ፡ ስለሚመጣ ፡ ክርስቶስ ፡ የግብፅን ፡
ሰዎች ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
፪፤ እሱ ፡ ተበቅሎ ፡ ያጠፋዋል ፡ በልቡናው ፡ ታብ
ይዋልና ፡ ጌትነቱን ፡ ወደ ፡ ጉስቁልናና ፡ ወደ ፡
መዋረድ ፡ ይመልሳል ።
፫፤ ወደ ፡ ባሕሩ ፡ መካከል ፡ እገባለሁና ፡ ወደ ፡ ሰማ
ይም ፡ እወጣለሁና ፡ ጥልቆችንም ፡ አያለሁና ፡
የአዳምን ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ ወፍ ፡ ጫጩት ፡
ጨጩብጨው ፡ እይዛቸዋለሁና ፡ ከኔ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡
የሚል ፡ ማነው ፡ ብሏልና ፡ ጌትነቱን ፡ ወደ ፡
ማዋረድ ፡ ይመልሰዋል ።
፬፤ ከቀናች ፡ ከሕገ ፡ እግዚአብሔር ፡ አርቃቸው ፡
ዘንድ ፡ በነሳቸው ፡ ምክንያት ፡ ስለ ፡ ሆንኩ ፡ የእ
ግዚአብሔርን ፡ ፈቃድ ፡ ካላደረጉ ፡ በዚህ ፡
ዓለም ፡ በሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ እኔ ፡ እበረታታባቸዋለ
ሁና ፡ ከሥልጣኔ ፡ የሚያስጥለኝ ፡ የለም ፡ አለ ።
ከኔ ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡ ሊሄዱ ፡ ጉጣጉጥ ፡ ፭፤
ወደ ፡ ሆነ ፡ ጉዳናም ፡ እመልሳቸው ፡ ዘንድ ፡
ምክንያት ፡ እሆናለሁና ።
የወደዱት ፡ ሕጉንም ፡ የጠበቁ ፡ ሰዎች ፡ ስለዚህ ፡ ፮፤
ነገር ፡ እኔን ፡ ይጠላሉ ፡ ከጌታቸው ፡ ሕግ ፡
ወጥተው ፡ የሳቱ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ወደኔ ፡ ይመ
ጣሉ ፡ እኔንም ፡ ይወዳሉ ፡ መሐላዬንም ፡ ይጠ
ብቃሉ ፡ እኔ ፡ ልቡናቸውን ፡ አከፋለሁና ፡ ወደ ፡
ፈጣሪያቸው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳይመ
ለሱ ፡ አሳባቸውንም ፡ እለውጣለሁና ፡ እኔ ፡ እን
ዳዘዝኋቸው ፡ ትእዛዜን ፡ ያደርጋሉ ።
የዚህን ፡ ዓለም ፡ ገንዘብ ፡ ባሳየኋቸውም ፡ ጊዜ ፡ ፯፤
ከቀናች ፡ ሕግ ፡ ልቡናቸውን ፡ አስታለሁ ፡ ቆንጆ
ችንና ፡ መልክ ፡ መልካም ፡ ሴቶችንም ፡ ባሳየኋ
ቸው ፡ ጊዜ ፡ በነዚህ ፡ ከቀናች ፡ ሕግ ፡ አርቃቸ

ዋለሁ ።
፰ የሚያበሩ ፡ የህንደኬ ፡ ዕንቁችንም ፡ ብርና ፡ ወር
ቅንም ፡ ባሳየኋቸው ፡ ጊዜ ፡ ወደኔ ፡ ሥራ ፡ ይመ
ለሱ ፡ ዘንድ ፡ በዚህም ፡ ከቀናች ፡ ሕግ ፡ አርቃ
ቸዋለሁ ።
፱ ቀጭን ፡ ልብስን ፡ ቀይ ፡ ሐርንና ፡ ነጭ ፡ ሐር
ንም ፡ ግምጃንና ፡ ነጭ ፡ ሐርንም ፡ ባሳየኋቸው ፡
ጊዜ ፡ በዚህም ፡ ከቀናች ፡ ሕግ ፡ አርቃቸዋለሁ ፡
ወደኔም ፡ አሳብ ፡ እመልሳቸዋለሁ ፡ ገንዘብን ፡
ከብቶችንም ፡ እንደ ፡ አሸዋ ፡ አብዝቼ ፡ ባሳየኋ
ቸው ፡ ጊዜ ፡ በዚህም ፡ ወደኔ ፡ ሥራ ፡ እመልሳ
ቸዋለሁ ።
፲ በትዕቢት ፡ ስለ ፡ ሴቶችም ፡ ስለ ፡ ቊጣና ፡ ስለ ፡
ጡብም ፡ የሚደረግ ፡ ቅናትን ፡ ባሳየኋቸው ፡ ጊዜ ፡
በዚህ ፡ ሁሉ ፡ ወደኔ ፡ ሥራ ፡ እመልሳቸዋለሁ ።
፲፩ ምልክቶችንም ፡ ባሳየኋቸው ፡ ጊዜ ፡ በባልንጀ
ሮቻቸው ፡ ልቡና ፡ አድራለሁ ፡ በልቡናቸውም ፡
እየራሱ ፡ የሆነ ፡ የምልክት ፡ ነገርን ፡ አሳድራ
ለሁ ፡ የቃላቸውንም ፡ ምልክት ፡ አሳይቼ ፡ አሳ
ትኋቸው ።
፲፪ ማደሪያዬንም ፡ ላደረኳቸው ፡ ሰዎች ፡ ምልክ
ትን ፡ አሳያቸዋለሁ ፡ በከዋክብት ፡ አካሄድም ፡
ቢሆን ፡ በደመና ፡ መውጣትም ፡ በእሳት ፡
ማናፋትም ፡ ቢሆን ፡ በአውሬዎችና ፡ በወፎ
ችም ፡ ጩኸት ፡ ቢሆን ፡ እነሳቸው ፡ ማደሪያ
ዎቼ ፡ ናቸውና ፡ በዚህ ፡ ሁሉ ፡ በልቡናቸው ፡
ምልክቶችን ፡ አሳድርባቸዋለሁ ።
፲፫ ተናግረው ፡ ለባልንጀሮቻቸው ፡ ምልክት ፡ ይሰ
ጧቸዋል ፡ እነዚያ ፡ ሟርተኞቻቸው ፡ እንደ ፡
ነገሯቸው ፡ እኔም ፡ ቀድሜ ፡ ምልክት ፡ እሆና
ቸዋለሁ ።
፲፬ የመረመሯቸው ፡ ሰዎች ፡ ይስቱ ፡ ዘንድ ፡ ለጠ
ንቋዮችም ፡ ዋጋን ፡ ይሰጧቸው ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡
ተናገሩት ፡ የሚደረግላቸው ፡ ትንቢትንም ፡ የሚ
ያውቁ ፡ ክፉና ፡ በጎንም ፡ የሚለዩ ፡ ሁሉም ፡
እንደ ፡ ተናገሩ ፡ የሚሆንላቸው ፡ እንደ ፡ ቃላቸ
ውም ፡ የሚደረግላቸው ፡ እንደ ፡ እገሌትና ፡
እንደ ፡ እገሌ ፡ አዋቆች ፡ የሉም ፡ ብለው ፡ ለባል
ንጀሮቻቸውም ፡ ይነግሯቸው ፡ ዘንድ ፡ የቃላቸ
ውን ፡ ምልክት ፡ አደርግላቸዋለሁ ።
፲፭ የሚጠፉ ፡ በኔም ፡ የሚስቱ ፡ ሰዎች ፡ ፈጽመው ፡
ይበዙ ፡ ዘንድ ፡ የአዳምም ፡ ልጆች ፡ ይጠፉ ፡
ዘንድ ፡ ይኸንን ፡ በተናገሩ ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ ደስ ፡
ይለኛል ፡ ለሚዋረድልኝ ፡ ለአዳም ፡ አልሰግ
ድም ፡ በማለቴ ፡ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ አባታ
ቸው ፡ ስለ ፡ አዳም ፡ ከማዕርጌ ፡ አዋርዶኛልና ።
፲፮ እኔም ፡ በትእዛዜ ፡ ጸንተው ፡ የሚኖሩ ፡ ልጆ
ቹን ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ጥፋት ፡ እወስዳቸዋለሁ ፡ ያሳ
ትኋቸው ፡ ሰዎች ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡
ይወርዱ ፡ ዘንድ ፡ ከፈጠረኝ ፡ ከእግዚአብሔር ፡
መሐላ ፡ አለኝ ።
፲፯ ቊጣውን ፡ በኔ ፡ በበዛ ፡ ጊዜ ፡ አሥረውም ፡ ወደ ፡
ገሃነም ፡ ይጥሉኝ ፡ ዘንድ ፡ ባዘዘ ፡ ጊዜ ፡ እንዲህ ፡
ብሎ ፡ ፈጣሪዬ ፡ ባዘዘ ፡ ጊዜ ፡ እኔም ፡ ጌታዬን ፡
ማለድኩ ፡ ተቈጥተኸኛልና ፡ በመቅሠፍትህም ፡
ገሥጸኸኛልና ፡ በመዓትህም ፡ ቀሥፈኸኛልና ፡
አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ በፊትህ ፡ አንዲት ፡ ነገር ፡ እና
ገር ፡ ዘንድ ፡ አሰናብተኝ ፡ እያልኩ ፡ በፊቱ ፡ ማለ
ድኩ ።
ጌታዬም ፡ ተናገር ፡ እሰማሃለሁ ፡ ብሎ ፡ መለሰ ፲፰
ልኝ ፡ ከማዕርጌ ፡ ከተዋረድኩ ፡ በኋላ ፡ ያሳትኳ
ቸው ፡ ሰዎች ፡ እኔ ፡ መከራ ፡ በምቀበልበት ፡
በገሃነም ፡ እንደኔ ፡ ይሁኑ ፡ ብዬ ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡
ወደሱ ፡ ልመናዬን ፡ ጀመርኩ ።
እሆቢ ፡ ያሉኝ ፡ በኔ ፡ ያልሳቱ ፡ ትእዛዝህን ፡ ያደ ፲፱
ርጉ ፡ ዘንድ ፡ ፈቃድህንም ፡ ይፈጽሙ ፡ ዘንድ ፡
ቃልህንም ፡ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ፡ ትእዛዜን ፡ ያል
ጠበቁ ፡ እኔ ፡ እንዳስተማርኳቸው ፡ እምቢ ፡
ብለው ፡ እኔ ፡ እንዳሳትኋቸው ፡ በኔ ፡ ባልሳቱ ፡
ጊዜ ፡ እነሳቸው ፡ ለጌትነትህ ፡ ይሁኑ ፡ በወደድ
ኸኝም ፡ ጊዜ ፡ ለኔ ፡ የሰጠኸኝን ፡ ዘውድ ፡ ይው
ሰዱ ።
ከኔ ፡ ጋራ ፡ የተሰደዱ ፡ ሰይጣናት ፡ የተባሉ ፡ ፳
የሥልጣናትን ፡ ዘውድ ፡ ለነሳቸው ፡ ስጣቸው ፡
ከኔ ፡ ከሠራዊቶቼም ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ በሆነች ፡
በዙፋኔ ፡ በቀኝህ ፡ አስቀምጣቸው ።
እንደ ፡ ወደድህም ፡ ያመስግኑህ ፡ እንደ ፡ ሠራ ፳፩
ዊቶቼና ፡ እንደኔም ፡ ይሁኑ ፡ እኔን ፡ ጠልተህ ፡
ከአመድና ፡ ከመሬት ፡ የተፈጠሩትን ፡ ስለ ፡ ወደ
ድካቸው ፡ የኔ ፡ ሥልጣን ፡ ጠፍቷልና ፡ የነሳ
ቸው ፡ ሥልጣን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብሏልና ፡ እንደ ፡
ወደድህ ፡ ያመስግኑህ ።
እያዩ ፡ እየሰሙ ፡ አንተ ፡ አስተሃቸዋልና ፡ ሥራ ፳፪
ዬን ፡ ሳይወዱ ፡ ከሳትሃቸው ፡ እንደ ፡ ፈቃድህ ፡
እንደ ፡ ቃልህ ፡ ይሁኑህ ፡ ብሎ ፡ ጌታዬ ፡ መለሰ
ልኝ ።
የመጻሕፍቶችን ፡ ቃልና ፡ ትእዛዜን ፡ ትተው ፡ ፳፫
ወዳንተ ፡ ከመጡ ፡ እኔንም ፡ ጥፋታቸው ፡ አያ
ሳዝነኝም ፡ አንተ ፡ ከሳትሃቸው ፡ በገሃነም ፡ እን
ዳንተ ፡ መከራ ፡ ይቀበሉ ፡ አለኝ ።
እስከ ፡ ዘላለሙ ፡ ድረስ ፡ በገሃነም ፡ መከራ ፡ ትቀ ፳፬
በላላችሁ ፡ እንጂ ፡ ላሳትካቸውና ፡ ላንተ ፡ ከገሃ
ነም ፡ እስከ ፡ ዘላለሙ ፡ ድረስ ፡ መውጫ ፡ የላች
ሁም ።

ምዕራፍ ፡ ፪ ።

አንተ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ብርያየ ፡ እንደ ፡ ኢዮብ ፡ ፩
ማሳት ፡ የተሳነህን ፡ እኔ ፡ በጌትነት ፡ ያንተን ፡
ዙፋን ፡ አወርሳቸዋለሁ ፡ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ አንተ ፡ ማሳት ፡ ለተሳነህ ፡ ሰዎች ፡
መንግሥት ፡ ሰማያትን ፡ እሰጣቸዋለሁ ፡ አለ ።
እኔም ፡ የአዳምን ፡ ልጆች ፡ በሁሉ ፡ እተነኰል ፪
ባቸዋለሁ ፡ እነሱን ፡ ማሳት ፡ ከተቻለኝ ፡ በበጎ ፡
ሥራ ፡ ይጸኑ ፡ ዘንድ ፡ አልተዋቸውም ፡ የአዳ
ምን ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ እተነኰልባቸዋለሁና ፡
የዚህን ፡ ዓለም ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ አጣፍጥላቸዋ
ለሁም ።
መጠጥንና ፡ መብልን ፡ ልብስንም ፡ በመውደድ ፡ ፫

ነገርንም ፡ በመውደድ ፡ በመንገትና ፡ በመስጠ
ትም ፡ ቢሆን ።
፬፤ መስማትና፡ማየትንም፡በመውደድ፡ቢሆን፡መዳ
ሰስና ፡ መሄድንም ፡ በመውደድ ፡ ቢሆን ፡ ትቢ
ትንና ፡ ነገርንም ፡ በማብዛት ፡ ቢሆን ፡ ሐሕም
ንና ፡ እንቅልፍንም ፡ በመውደድ ፡ ቢሆን ።
፭፤ ስካርንና ፡ መጠጥንም ፡ በማብዛት ፡ ቢሆን ፡ ስድ
ብንና ፡ ቍጣንም ፡ በማብዛት ፡ ቢሆን ፡ ጨዋታ
ንና ፡ ያልረባ ፡ ነገርን ፡ በመናገር ፡ ቢሆን ።
፮፤ በጠብ ፡ ባልንጀራቸውንም ፡ በማማት ፡ ቢሆን ፡
መልክ፡ መልክሞች ፡ የሆኑ ፡ የዚህን ፡ ዓለም ፡
ሴቶችን ፡ በማየትም ፡ ቢሆን ፡ የሚያስቷቸው ፡
የሸቱዎችን ፡ መዓዛ ፡ በማሽተት ፡ ቢሆን ።
፯፤ መዳንን ፡ እንዳይችሉ ፡ በዚህ ፡ ሁሉ ፡ እኔ ፡ እጠ
ላቸዋለሁ ፡ ስለሳቸው ፡ ከማሰርጌ ፡ የተዋረደሁ
በት ፡ ወደ ፡ ጥፋት ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ይገቡ ፡ ዘንድ ፡
ከእግዚአብሔር ፡ ሕግ፡ አርቃቸዋለሁ ።
፰፤ ነቢዩም ፡ ሰውን ፡ የምታጠፋ ፡ አንተ ፡ ጥፋ ፡
በልቡናህ ፡ ጽናትና ፡ በትዕቢትህ ፡ በልቡናህ ፡
ጽናት ፡ ፈጣሪህንም ፡ በማሳዘን ፡ ፈጣሪህንም ፡
ባለማመስገን ፡ አንተ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ትእ
ዛዝ ፡ ወጥተህ ፡ በወነጀልህ ፡ ጊዜ ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ ፍጥረት ፡ ላይ ፡ አንተ ፡ እንዲህን ፡ ትታ
በያለህን ፡ አለው ።
፱፤ ፈጣሪህ ፡ በተቈጣህ ፡ ጊዜ ፡ ስለ ፡ ክፉ ፡ ሥራህ ፡
ከማዕርግህ ፡ አዋረደህ ፡ ፈጣሪው ፡ ከመሬት ፡
የፈጠረውን ፡ እንደወደደ ፡ ያደረገውን ፡ ለምስ
ጋናውም ፡ ያኖረውን ፡ አዳምን ፡ ወደ ፡ ኃጢ
አት ፡ ለምን ፡ ትወስደዋለህ ፡ አለው ።
፲፤ ረቂቅ ፡ የምትሆን ፡ ከነፋስና ፡ ከእሳት ፡ የተፈ
ጠርህ ፡ አንተ ፡ ፈጣሪ ፡ ነኝ ፡ በማለት ፡ በታበ
ይህ ፡ ጊዜ ።
፲፩፤ አንተ ፡ በተመካህ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ክፉ ፡
ሥራህን ፡ አይቶ ፡ አንተ ፡ ከሠራዊቶችህ ፡ ጋራ ፡
እግዚአብሔርን ፡ ክደሃልና ፡ ሳያቋርጥ ፡ ስሙን ፡
ያመሰግን ፡ ዘንድ ፡ ስላንተ ፡ ፈንታ ፡ የሚያመስ
ግን ፡ አዳምን ፡ ፈጠረው ።
፲፪፤ እንዳንተ ፡ ከሉ ፡ ከመላእክት ፡ ሠራዊት ፡ ሁሉ ፡
ይልቅ ፡ ራስህን ፡ አከብርተሃልና ፡ ስለ ፡ ትዕቢ
ትህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከናቃቸው ፡ ከሠራዊቶ
ችህ ፡ ጋራ ፡ አንተ ፡ ስለምታመሰግነው ፡ ምስ
ጋና ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ ያመሰግኑ ፡ ዘንድ ፡
አዳምን ፡ ከልጆቹ ፡ ጋራ ፡ ፈጠረው ።
፲፫፤ ስለዚህም ፡ ነገር ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳንተ ፡
ከሉ ፡ ከመላእክት ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡ ለይቶ ፡ አጠ
ፋህ ፡ ባንድ ፡ ምክር ፡ ከንተ ፡ ጋራ ፡ የተፈጠሩ ፡
ሠራዊቶችህና ፡ አንተም ፡ ስለማይጠቅም ፡ ስለ ፡
ልቡናችሁ ፡ ትዕቢትና ፡ ስለ ፡ ልቡናችሁ ፡ ጽናት ፡
ከእግዚአብሔር ፡ ምስጋና ፡ ወጥታችሁ ፡ ስታ
ችሁ ፡ በሌላ ፡ ያይደለ ፡ በፈጣሪያችሁም ፡ ላይ ፡
ታበያችሁ ።
፲፬፤ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ በተዋረዱ ፡ ሰዎች ፡ ይመሰገን ፡
ዘንድ ፡ አዳምን ፡ ከመሬት ፡ ፈጠረው ፡ ከበለስ ፡
ፍሬ ፡ እንዳይበላ ፡ አትብላ ፡ ብሎ ፡ ትእዛዝና ፡
ሕግንም ፡ ሰጠው ።
በፈጠረው ፡ ፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ ላይም ፡ ሾመው ፡ ፲፭፤
በራስህ ፡ ሞትን ፡ እንዳታመጣ ፡ ሞትን ፡ ከምታ
መጣ ፡ ከንዲት ፡ በለስ ፡ ፍሬ ፡ አትብላ ፡ እንጂ ፡
በገነት ፡ መካከል ፡ ካለው ፡ እንጨት ፡ ሁሉ ፡
ፍሬ ፡ ብላ ፡ ብሎ ፡ ልብ ፡ አስደረገው ።
ይህቹንም ፡ ቃልን ፡ በሰማሃት ፡ ጊዜ ፡ ከአዳም ፡ ፲፮፤
ጐን ፡ አጥንት ፡ ለተገኘች ፡ ለሔዋን ፡ ባንደበ
ትህ ፡ ከተናገርከው ፡ ነገር ፡ የተነግ ፡ ክሕደትን ፡
አሳደርህበት ።
እንዳንተ ፡ ሕግ ፡ አፍራሽ ፡ ታደርገው ፡ ዘንድ ፡ ፲፯፤
በጽኑ ፡ ክዳት ፡ ንጹሕ ፡ የሆነ ፡ አዳምን ፡ አሳት
ከው ።
እንደ ፡ የዋህ ፡ ርግብ ፡ ሁና ፡ የተፈጠረች ፡ ተን ፡ ፲፰፤
ኰልህን ፡ የማታውቅ ፡ ሔዋንን ፡ ባሳትከት ፡
ጊዜ ፡ በተከናወነ ፡ ነገርህና ፡ በጠማማ ፡ ቃልህ ፡
አስከድከት ፡ አስቀድማ ፡ የተፈጠረች ፡ ያችንም ፡
ሔዋንን ፡ ከሳትከት ፡ በኋላ ፡ እሷም ፡ ሄዳ ፡ አስ
ቀድሞ ፡ ከመሬት ፡ የተፈጠረ ፡ የእግዚአብሔር ፡
ፍጥረት ፡ አዳምን ፡ አሳተችው ።
በትዕቢትህም ፡ ያይደለ ፡ ሁከት ፡ አስከድከው ፡ ፲፱፤
የፈጣሪውንም ፡ ቃል ፡ ይክድ ፡ ዘንድ ፡ እንዲ
ክድ ፡ አደረግኸው ፡ በትዕቢትህም ፡ አዳምን ፡
አጠፋኸው ።
በተንኰልህም ፡ ከፈጣሪው ፡ ፍቅር ፡ አራቅ ፡ ፳፤
ኸው ፡ በምክንያትህም ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ካለ
በት ፡ ከገነት ፡ አወጣኸው ፡ በመሰናክልህም ፡
የገነትን ፡ መብል ፡ አስተውከው ።
አንተ ፡ ፍዳ ፡ ወደምትቀበልበት ፡ ወደ ፡ ሲኦል ፡ ፳፩፤
ታወርደው ፡ ዘንድ ፡ ከለመኖር ፡ ወደ ፡ እውነት
ኛው ፡ መኖር ፡ ከመጣው ፡ ከፈጠረውም ፡ ፍቅር ፡
ታወጣው ፡ ዘንድ ፡ የዋህ ፡ ፍጥረት ፡ አዳምን ፡
ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ አንተ ፡ ተጣልተኸዋልና ፡
ባሰተኛ ፡ ነገርህም ፡ ከገነት ፡ መጠጥ ፡ አስጠማ
ኸው ።
መሬታዊም ፡ ሲሆን ፡ በሥጋውና ፡ በነፍሱ ፡ ፳፪፤
በልቡናውም ፡ ፈጣሪውን ፡ ፈጽሞ ፡ የሚያመ
ሰግን ፡ የረቀቀ ፡ መልአክን ፡ አደረገው ።
በገናዎች ፡ በየስልታቸው ፡ እንደሚያመሰግኑ ፡ ፳፫፤
ብዙ ፡ አሳቦችንም ፡ ፈጠረለት ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

ፈጣሪህ ፡ ወደላከህ ፡ እየተላክህ ፡ ፈጽመህ ፡ ፩፤
ታመሰግን ፡ ዘንድ ፡ ላንተ ፡ ግን ፡ አንድ ፡ አሳ
ብን ፡ ፈጠረልህ ።
ለአዳም ፡ ግን ፡ ክፉ ፡ የሆኑ ፡ አምስት ፡ አሳቦችና ፡ ፪፤
በጎ ፡ የሆኑ ፡ አምስት ፡ አሳቦች ፡ አሥር ፡ አሳ
ቦች ፡ ተሰጡት ።
ዳግመኛም ፡ እንደ ፡ ባሕር ፡ ሞገድ ፡ ከምድር ፡ ፫፤
እንሥቶ ፡ ትቢያን ፡ እንደሚበትን ፡ ጥቅል ፡ ነፋ
ስም ፡ እንደሚያናውጠው ፡ እንደ ፡ ባሕር ፡ ሞገ
ድም ፡ ብዙ ፡ አሳቦች ፡ አሉት ፡ እንደማይቈጠር ፡
እንደ ፡ ዝናብም ፡ ጠብታ ፡ በልቡ ፡ ካለ ፡ ከማይ
ቈጠር ፡ ከሳቡ ፡ ብዛት ፡ የተነግ ፡ የአዳም ፡ አሳብ ፡

እንደዚያ ፡ ነው ፡፡
፬ ፡ አንተ ፡ ግን ፡ አሳብህ ፡ እንዲት ፡ ናት ፡ ሥጋዊ ፡
አይደለህምና ፡ ሌላ ፡ አሳብ ፡ የለህም ፡፡
፭ ፡ አንተ ፡ ግን ፡ በእብብ ፡ ልቡና ፡ አድረህ ፡ በክፉ ፡
ክደት ፡ አንድ ፡ አካል ፡ የሆነ ፡ አዳምን ፡ አጠፋ
ኸው ፡ ሔዋንም ፡ የብብን ፡ ነገር ፡ ሰማች ፡ ሰም
ታም ፡ እንዳዘዘቻት ፡ አደረገች ፡፡
፮ ፡ የበለስ ፡ ፍሬን ፡ ከበላች ፡ በኋላ ፡ መዋታ ፡
የእግዚአብሔር ፡ መጀመሪያ ፡ ፍጥረቱ ፡ አዳ
ምን ፡ አሳተችው ፡ የፈጣሪዋን ፡ ትእዛዝ ፡ ስለ ፡
ተደፋፈረች ፡ በሱም ፡ በልጆቹም ፡ ሞትን ፡
አመጣች ፡፡
፯ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በውነተኛ ፡ ፍርዱ ፡ ከገነት ፡
ወጡ ፡ በተሰደዱበት ፡ ምድር ፡ ከባሕርያቸው ፡
በተወለዱ ፡ ልጆቻቸው ፡ ከምድር ፡ በተገኘ ፡
አዝመራቸውም ፡ አረጋጋቸው ፡ እንጂ ፡ ተጣ
ልቶ ፡ ከገነት ፡ አላራቃቸውም ፡፡
፰ ፡ ቀንተህም ፡ ከገነት ፡ በስወጣሀቸው ፡ ጊዜ ፡ ሊረ
ጋጉ ፡ ተክልና ፡ ልጅን ፡ ከመሬትነቷ ፡ ምድር ፡
ባስገኘችው ፡ በምደር ፡ ፍሬም ፡ ልቡናቸውን ፡
ሊያድሱ ፡ ይተክሉ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡
በሰጣቸው ፡ በምድር ፡ ፍሬና ፡ በገነት ፡ ፍሬም ፡
ይረጋጉ ፡ ዘንድ ፡፡
፱ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከገነት ፡ እንጨት ፡ የለመለሙ ፡
እንጨቶችን ፡ ሰጣቸው ፡ እሱንም ፡ በበሉ ፡
ከገነት ፡ ያወጣሃቸው ፡ ሔዋንና ፡ አዳም ፡ ከኃ
ዘን ፡ ፈጽመው ፡ ይረጋጋሉ ፡፡
፲ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፍጥረቱን ፡ ማረጋጋት ፡ ያውቃ
ልና ፡ ስለ ፡ ልጆቻቸው ፡ ከምድር ፡ ስለተገኘው ፡
አዝመራም ፡ ልቡናቸው ፡ ይረጋጋል ፡፡
፲፩ ፡ አሚከላና ፡ እሾህ ፡ ወደምታበቅል ፡ ወደዚች ፡
ዓለም ፡ ተሰደዋልና ፡ ልቡናቸውን ፡ በውሀና ፡
በእህል ፡ ያጸናሉ ፡፡

ምዕራፍ ፡ ፬ ፡፡

፩ ፡ ጌታው ፡ አዳምን ፡ ይቤ፲ው ፡ ዘንድ ፡ አለው ፡
አንተንም ፡ ያሳፍርሀል ፡ በግን ፡ ከተኰላ ፡ አፍ ፡
ያድነዋል ፡ (አዳምን ፡ ከዲያብሎስ) ፡፡
፪ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ አንተ ፡ የገዛሀቸውን ፡ ሰዎች ፡ ከንተ ፡
ጋራ ፡ ይዘህ ፡ ወደገሃነም ፡ ትሔዳለህ ፡፡
፫ ፡ የፈጣሪያቸው ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ የጠ
በቁ ፡ ሰዎች ፡ የሱ ፡ እድል ፡ ያደርጋቸው ፡ ዘንድ ፡
የፈጣሪያቸው ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ሕግ ፡
እንዳንተ ፡ ካልተደፋፈሩ ፡ ከከበሩ ፡ ከመላእክ
ትም ፡ ጋራ ፡ ያመሰግኑት ፡ ዘንድ ፡ ከክፉ ፡ ሥራ ፡
ከሠወራቸው ፡ ከፈጣሪያቸው ፡ ከእግዚአብ
ሔር ፡ ጋራ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፡፡
፬ ፡ ከአገልጋዮቹ ፡ ከመላእክት ፡ ጋራ ፡ ታመስግ
ነው ፡ ዘንድ ፡ እንዳንተ ፡ ካሉ ፡ ከመላእክት ፡
ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ መርጦ ፡ የሰጠህ ፡ እግዚአብሔር ፡
አንተ ፡ ግን ፡ በትቢትህ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ዙፋንን ፡
ነሳህ ፡፡
፭ ፡ አንተ ፡ ግን ፡ ገነንህ ፡ እምላክነትንም ፡ የሚወድ ፡
ተብልህ ፡ ሠራዊቶችህም ፡ አጋንንት ፡ ተብሉ ፡፡
እግዚአብሔርን ፡ የሚወዱ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ እን ፡ ፮ ፡
ደከበሩ ፡ እንደ ፡ መላእክት ፡ ወገኖቹን ፡ ይሆ
ናሉ ፡ የሚያመሰግኑት ፡ ሱራፌልና ፡ ኪሩቤ
ልም ፡ ከንፋቸውን ፡ ዘርግተው ፡ ያለበዘን ፡
ያመሰግናሉ ፡፡
አንተ ፡ ግን ፡ በመልክህ ፡ ከተፈጠሩ ፡ ከሠራዊ ፡ ፯ ፡
ትህና ፡ ከወገኖችህ ፡ ጋራ ፡ ሁለጊዜ ፡ ታመስግ
ነው ፡ ዘንድ ፡ ምስጋናህን ፡ በትቢትህና ፡ በስን
ፍናህ ፡ አጠፋህ ፡፡
እንዳንተ ፡ ያለ ፡ ፍጥረት ፡ መፍጠር ፡ የማይቻ ፡ ፰ ፡
ለው ፡ መስሎህ ፡ አንተ ፡ የፈጠረህ ፡ የእግዚአ
ብሔርን ፡ ምስጋና ፡ በዘነጋህ ፡ ጊዜ ፡ አሥረኛ ፡
ነገድ ፡ አድርጎ ፡ የፈጠረህ ፡ የእግዚአብሔር ፡
ምስጋናው ፡ እንዳይጐድል ፡ አንተም ፡ ከወንድ
ሞችህ ፡ አንድነት ፡ በተለየህ ፡ ጊዜ ፡ የፈጠረህ ፡
የእግዚአብሔር ፡ ምስጋናው ፡ እንዳይጐድል ፡
ስላንተ ፡ ፈንታ ፡ አዳምን ፡ ፈጠረ ፡፡
አንተ ፡ ግን ፡ በልቡናህ ፡ ትዕቢት ፡ የፈጠረህ ፡ ፱ ፡
የእግዚአብሔርን ፡ ምስጋና ፡ ቸል ፡ አልህ ፡
እሱም ፡ ተቈጣህ ፡ ተዘበበተብህ ፡ አሥሮም ፡
ከሠራዊቶችህም ፡ ጋራ ፡ በገሃነም ፡ አጋዘህ ፡፡
በከበሩ ፡ እጆቹ ፡ ከምድር ፡ መሬትን ፡ አምጥቶ ፡ ፲ ፡
እሳትና ፡ ውኃን ፡ ነፋስንም ፡ ጨምሮ ፡ በሱ ፡
ምሳሌና ፡ መልክ ፡ አዳምን ፡ ፈጠረው ፡፡
ምስጋናው ፡ አንተ ፡ ታመሰግነው ፡ በነበረ ፡ ምስ ፡ ፲፩ ፡
ጋና ፡ ይመላ ፡ ዘንድ ፡ በሥልጣኑ ፡ በፈጠረው ፡
ፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ ሾመው ፡ የአዳም ፡ ምስጋና ፡
ከመላእክት ፡ ምስጋና ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ሆነ ፡ ምስ
ጋናቸውም ፡ የተከከለ ፡ ሆነ ፡፡
አንተ ፡ ግን ፡ በክፋደ ፡ ልቡናህ ፡ ጽናትና ፡ በትዕ ፡ ፲፪ ፡
ቢትህ ፡ ከማዕርግህ ፡ ተዋርደህ ፡ ከፈጠረህ ፡
ከእግዚአብሔር ፡ ጌትነት ፡ ወጥተህ ፡ ራስህን ፡
አጠፋህ ፡፡
የእግዚአብሔርነቱ ፡ ምስጋና ፡ እንዳይጐድል ፡ ፲፫ ፡
እግዚአብሔር ፡ በልቡናው ፡ ምክር ፡ የሚያመ
ሰግነው ፡ አዳምን ፡ ፈጥሯልና ፡ ምስጋናው ፡
እንዳልጐደለ ፡ እወቅ ፡፡
እርሱ ፡ ሳይደረግ ፡ ሁሉን ፡ ያውቃልና ፡ ትእዛ ፡ ፲፬ ፡
ዙንም ፡ እንድታፈርስ ፡ ሳይፈጥርህ ፡ አወቀህ ፡
ዓለም ፡ ሳይፈጠር ፡ በርሱ ፡ ዘንድ ፡ የተሰወረ ፡
ምክር ፡ አለና ፡ በካደኸው ፡ ጊዜ ፡ በርያው ፡
አዳምን ፡ በመልኩ ፡ በምሳሌው ፡ ፈጠረው ፡፡
ሰሎሞን ፡ ክረምቶች ፡ ሳይፈጠሩ ፡ ዓለምም ፡ ፲፭ ፡
ተፈጥሮ ፡ ሳይከናወን ፡ የምድር ፡ መሠረቶች ፡
የሚሆኑ ፡ ነፋሶችንም ፡ ሳይፈጥር ፡፡
የከረብቶችና ፡ የተራራዎችንም ፡ መሠረት ፡ ፲፮ ፡
ሳያጸና ፡ የዚህም ፡ ዓለም ፡ ሥራ ፡ ሳይጸና ፡ የጨ
ረቃና ፡ የፀሐይም ፡ ብርሃን ፡ ሳይበራ ፡ የዘመኖ
ችና ፡ የከዋክብት ፡ ምግብና ፡ ሳይታወቅ ፡፡
መዓልትና ፡ ሌሊትም ፡ ሳይፈራረቁ ፡ ባሕርም ፡ ፲፯ ፡
ባሸዋ ፡ ሳትወሰን ፡ የተፈጠረው ፡ ፍጥረት ፡
ሁሉ ፡ ሳይፈጠር ፡፡
ዘሬም ፡ የሚታየው ፡ ሁሉ ፡ ሳይታይ ፡ ዛሬ ፡ የሚ ፡ ፲፰ ፡
ጠራው ፡ ስም ፡ ሁሉ ፡ ሳይጠራ ፡ ሰሎሞን ፡ ፈጠ

ረኝ ፡ ብሎ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ እንዳንተ ፡ ያሉ ፡
መላእክትና ፡ አንተ ፡ በርያው ፡ አዳምም ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ ልቡና ፡ ነበራችሁ ።
፲፱ ፡ አንተ ፡ በክድህ ፡ ጊዜ ፡ የከበረ ፡ ስሙ ፡ ይመሰ
ገን ፡ ዘንድ ፡ አንተም ፡ በታበይህ ፡ ጊዜ ፡ ከመ
ሬት ፡ በተፈጠረ ፡ በተዋረደ ፡ በበርያው ፡ በአ
ዳም ፡ ይመሰገን ፡ ዘንድ ፡ አዳምን ፡ ፈጠረው ።
፳ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሰማይ ፡ ሁኖ ፡ የድሆችን ፡
ልመና ፡ ይሰማልና ፡ የተዋረዱ ፡ ሰዎችንም ፡
ምስጋና ፡ ይወዳል ።
፳፩ ፡ በሚፈሩት ፡ ሰዎች ፡ አድሮ ፡ ማዳን ፡ ይወዳል ፡
እንጂ ፡ የፈረስን ፡ ኃይል ፡ አይወድምና ፡ ጭን ፡
ጥብቅም ፡ ብሎ ፡ አይፈመድምና ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ የትቢተኞችን ፡ ነገር ፡ ቻል ፡ ይላል ።
፳፪ ፡ ስለ ፡ ሠሩት ፡ ኃጢአታቸውም ፡ እየሮጡ ፡ ያለ
ቅሳሉ ።
፳፫ ፡ አንተ ፡ በንስሐ ፡ መለማመጥ ፡ ተሳንህ ።
፳፬ ፡ ከመሬት ፡ የተፈጠረ ፡ አዳም ፡ ግን ፡ ስለ ፡ ኃጢ
አቱ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ፈጽሞ ፡ እያለ
ቀሰ ፡ በንስሐ ፡ ተመለሰ ።
፳፭ ፡ አንተ ፡ ግን ፡ በክፋደ ፡ ልቡናህ ፡ ጽናትና ፡ በል
ብህ ፡ ትቢት ፡ የፍቅር ፡ ሥራን ፡ አላወቅሃትም ፡
ንስሐንም ፡ አላወቅሃትም ፡ በንስሐ ፡ በልቅሶና ፡
በኀዘንም ፡ በፈጣሪህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
መለማመጥ ፡ ተሳንህ ።
፳፮ ፡ አመድ ፡ መሬት ፡ የሚሆን ፡ ያ ፡ አዳም ፡ ግን ፡
በልቅሶና ፡ በኀዘን ፡ ወደ ፡ ንስሐ ፡ ተመለሰ ፡
ወደ ፡ ትሕትናና ፡ ወደ ፡ ፍቅርም ፡ ሥራ ፡ ተመ
ለሰ ።
፳፯ ፡ አንተ ፡ ግን ፡ ለፈጠረህ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ልቡ
ናህንና ፡ ራስህን ፡ አላዋረድህም ።
፳፰ ፡ አዳምስ ፡ በበደለው ፡ በደል ፡ ራሱን ፡ አዋርዶ ፡
ተለማመጠ ፡ አልከራም ።
፳፱ ፡ ወንጀልን ፡ አንተ ፡ ፈጽመህ ፡ አስገኘተኸዋልና ፡
ከንተ ፡ ተገኘ ፡ እንጂ ፡ ያንንም ፡ ስሕተት ፡ እሱ ፡
ያስገኘው ፡ አይደለም ፡ በትቢትህ ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡
ወዳንተ ፡ ጥፋት ፡ ወሰድከው ።
፴ ፡ ሁላታችሁን ፡ ሁሉ ፡ ሳይፈጥራችሁ ፡ ኃጢአ
ተኞች ፡ እንደሆናችሁ ፡ አውቋችኋልና ፡ ሥራ
ችሁንም ፡ አውቋልና ፡ ይህ ፡ የተደረገ ፡ በልብህ ፡
ትቢት ፡ እንደሆነ ፡ እሱ ፡ ያውቃል ።
፴፩ ፡ ያ ፡ ትቢት ፡ ተንኮል ፡ የሌለው ፡ አዳምን ፡ ግን ፡
በንስሐ ፡ በልቅሶ ፡ በኃዘን ፡ መለሰው ።
፴፪ ፡ በድሎ ፡ በንስሐ ፡ የማይለማመጥ ፡ ሰው ፡ ከቀ
ድሞ ፡ በደሉ ፡ ይልቅ ፡ በደሉን ፡ አብዝቷልና ፡
አንተ ፡ ግን ፡ በልብህ ፡ ትቢት ፡ በንስሐ ፡ መለ
ማመጥ ፡ ተሳንህ ፡ በፈጣሪው ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ በንስሐ ፡ ገብቶ ፡ የሚለማመጥ ፡ የሚያለ
ቅስ ፡ ሰው ፡ ግን ።
፴፫ ፡ እሱ ፡ በውነት ፡ ንስሐ ፡ ገባ ፡ የጌታውን ፡ ልብ ፡
ይፈራ ፡ ዘንድ ፡ የሚድንበትንም ፡ ሥራ ፡ አገኘ ፡
በፈጣሪውም ፡ ፊት ፡ ተለማመጠ ፡ በመስገድና ፡
በብዙ ፡ ንስሐ ፡ በፊቱ ፡ ተለማምጧልና ፡ በባር
ያው ፡ እንዳይቈጣ ፡ ጌታውም ፡ ከቀደመው ፡
መከራ ፡ የተነሣ ፡ ኃጢአቱን ፡ ያቃልልለታል ፡
የቀደመው ፡ ኃጢአቱንም ፡ ይቅር ፡ ይለዋል ።
ወደ ፡ ቀድሞ ፡ ኃጢአቱ ፡ ካልተመለሰ ፡ ይኸን ፴፬
ንም ፡ ከደረገ ፡ ይህ ፡ ፍጹም ፡ ንስሐ ፡ ነው ፡
አዳም ፡ ፈጣሪውን ፡ ማሰብ ፡ የፈጠረው ፡ እግዚ
አብሔርንም ፡ በንስሐ ፡ መለማመጥ ፡ አልዘነ
ጋም ።
አንተም ፡ ወደ ፡ ፈጣሪህ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፴፭
በንስሐ ፡ ተለማመጥ ፡ እነሱንም ፡ ሥጋዊ ፡
ደማዊ ፡ ስለሆኑ ፡ አትበድል ፡ የፈጠራቸው ፡
እግዚአብሔር ፡ ይከማቸውን ፡ ያውቃልና ፡
በሥልጣኑም ፡ የፈጠራቸውን ፡ ሰዎች ፡ አት
በድል ።
ነፍሳቸውም ፡ ከሥጋቸው ፡ ከተለየች ፡ በኋላ ፡ ፴፮
እግዚአብሔር ፡ እስከሚወዳት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡
ሥጋቸው ፡ ትቢያ ፡ ይሆናል ።

ምዕራፍ ፡ ፫ ።

የፈጠረህ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እወቀው ፡ አንተ ፡ ፩
መሬት ፡ ስትሆን ፡ በመልኩ ፡ በምሳሌው ፡ ፈጥሮ
ሃልና ፡ ያዐናህ ፡ ያዳነህ ፡ እስራኤል ፡ ያከበሩት ፡
እግዚአብሔርን ፡ አትርሳው ፡ ደስ ፡ ይልህ ፡
ዘንድ ፡ ምድርንም ፡ ትቆፍራት ፡ ዘንድ ፡ በገ
ነት ፡ አኖረህ ።
ትእዛዙን ፡ በፈረስህ ፡ ጊዜ ፡ ከገነት ፡ አሚከላና ፡ ፪
እሾህ ፡ ወደምታበቅል ፡ ስላንተ ፡ ወደረገማት ፡
ወደዚች ፡ ዓለም ፡ አወጣህ ።
አንተ ፡ ምድር ፡ ነህና ፡ እሷም ፡ ምድር ፡ ናትና ፡ ፫
አንተ ፡ ትቢያ ፡ ነህና ፡ እሷም ፡ ትቢያ ፡ ናትና ፡
አንተ ፡ መሬት ፡ ነህና ፡ እሷም ፡ መሬት ፡ ናትና ፡
ከሷ ፡ የተገኘውን ፡ እህል ፡ ትመገበለህና ፡ ወደ
ሷም ፡ ትመለሳለህና ፡ ያነሣህ ፡ ዘንድ ፡ እስኪ
ወድ ፡ ድረስ ፡ መሬት ፡ ትሆናለህና ፡ የሠራኸ
ውን ፡ ኃጢአትና ፡ በደሉንም ፡ ሁሉ ፡ ይመረ
ምርሃልና ።
የዚያን ፡ ጊዜ ፡ የምትመልሰውን ፡ እወቅ ፡ በዚህ ፡ ፬
ዓለም ፡ የሠራኸውን ፡ በጎውንና ፡ ክፉውንም ፡
አስብ ፡ ክፉውም ፡ ይበዛ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በጎውም ፡
ይበዛ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ መርምር ፡ ሞክር ።
በጎ ፡ ነገር ፡ ብትሠራ ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ በሚነሡ ፡ ፭
በት ፡ ቀን ፡ ደስ ፡ ይልህ ፡ ዘንድ ፡ ላንተ ፡ በጎ ፡
ነገር ፡ ነው ።
ክፉ ፡ ሥራ ፡ ብትሠራ ፡ ግን ፡ ወዮልህ ፡ እንደ ፡ ፮
እጅህ ፡ ሥራ ፡ እንደ ፡ ልቡናህም ፡ ክፋት ፡ ፍዳ
ህን ፡ ትቀበላለህና ፡ በባልንጀራህ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡
ብትሠራበት ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ካልፈራኸው ፡
ፍዳህን ፡ ትቀበላለህና ።
ባልንጀራህንም ፡ ብትከዳው ፡ የእግዚአብሔር ፯
ንም ፡ ስም ፡ ጠርተህ ፡ በሐሰት ፡ ብትምል ፡ እንደ ፡
ሥራህ ፡ ፍዳህን ፡ ትቀበላለህና ፡ ወዮልህ ።
ሐሰተኛውንም ፡ ነገርህን ፡ ለባልንጀራህ ፡ እው ፰
ነት ፡ አስመስለህ ፡ ትነግረዋለህ ፡ አንተ ፡ ግን ፡
አሰት ፡ እንደ ፡ ተናገርህ ፡ ታውቀዋለህ ።
ካንተ ፡ ጋራ ፡ ያሉትንም ፡ ሰዎች ፡ አሰተኛውን ፡ ፱

ነገርህን ፡ እውነት ፡ አስመስለህ ፡ ታሰምናቸዋ
ለህ ፡ እውነት ፡ ያልሆነ ፡ ሐሰተኛ ፡ ነገርንም ፡
ታበዛለህ ፡ እንደ ፡ ኃጢአትህም ፡ ፍዳህን ፡ ትቀ
በላለህ ፡ የማትሰጠውን ፡ ለባልንጀራህ ፡ እሰጥ
ሃለሁ ፡ እያልክ ፡ ባልንጀራህን ፡ ትከዳዋለህ ።
፲፤ በንጹሕ ፡ ልቡናህም ፡ እሰጣለሁ ፡ ባልህ ፡ ጊዜ ፡
አጋንንት ፡ እንደ ፡ ውሾች ፡ ደጅ ፡ ይጠኑሃል ፡
ሁሉንም ፡ ያስረሱሃል ፡ ብትነሣም ፡ ትሰጥ ፡
ዘንድ ፡ ብትወድም ፡ የሚሰበስቡለትን ፡ ሰው ፡
አያውቁትም ፡ እንጂ ፡ ያደልበሉ ፡ ብሏልና ፡
የማይጠቅምህ ፡ የማትበላውን ፡ ገንዘብ ፡ ታደ
ልብ ፡ ዘንድ ፡ የዚህ ፡ ዓለም ፡ ገንዘብ ፡ ያስጐመ
ጅሃል ።
፲፩፤ ዳግመኛም ፡ አሰተኞች ፡ የአዳም ፡ ልጆች ፡ ሚዛ
ንን ፡ ሐሰተኛ ፡ ያደርጋሉ ፡ እነሱቸውስ ፡ ከቀ
ሚያ ፡ ወደ ፡ ቅሚያ ፡ ይሄዳሉ ፡ ብሏልና ፡ የዚህ ፡
ዓለም ፡ ገንዘብ ፡ ያስጐመጅሃል ።
፲፪፤ ሰዎች ፡ ሆይ ፡ ላዳንና ፡ ሚዛንን ፡ በማሳበል ፡
የሰውንም ፡ ገንዘብ ፡ በመስረቅ ፡ በግፍም ፡ የሰው ፡
ገንዘብ ፡ አንድ ፡ በማድረግ ፡ የባልንጀራችሁ
ንም ፡ ገንዘብ ፡ በመደፋፈር ፡ እርሻውንም ፡ በመ
ስረቅ ፡ ለባልንጀራችሁ ፡ ያይደለ ፡ ለራሳችሁ ፡
ትርፍ ፡ በምታደርጉት ፡ ሁሉ ፡ ሐሰትን ፡ ተስፋ ፡
አታድርጉት ።
፲፫፤ ይኸንን ፡ ብታደርጉ ፡ እንደ ፡ ሥራችሁ ፡ ፍዳ
ችሁን ፡ ትቀበላላችሁ ።
፲፬፤ ሰዎች ፡ ሆይ ፡ የቀና ፡ በሆነ ፡ በጃችሁ ፡ ሥራ ፡
ተመገቡ ፡ እንጂ ፡ ቅሚያን ፡ አትመኟት ፡ በማይ
ገባ ፡ ያለ ፡ ፍርድ ፡ ፈጽማችሁ ፡ ቀምታችሁ ፡
የሰውን ፡ ገንዘብ ፡ ትበሉ ፡ ዘንድ ፡ አትውደዱ ።
፲፭፤ ብትበሉትም ፡ አያጠግባችሁም ፡ በሞታችሁ ፡
ጊዜ ፡ ለሌላ ፡ ትተውታላችሁ ፡ እንጂ ፡ ብታደል
ቡም ፡ አይጠቅማችሁም ።
፲፮፤ ገንዘባችሁም ፡ ቢበዛ ፡ ልቡናችሁን ፡ አታሳብዩ ፡
የኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ ገንዘብ ፡ ከምድጃ ፡ እንደ
ሚወጣ ፡ ነፋስም ፡ እንደሚወስደው ፡ እንደ ፡
ጢስ ፡ ነውና ፡ ብዙ ፡ ከሆኑ ፡ ከኃጢአተኞች ፡
ሰዎች ፡ ገንዘብ ፡ በውነት ፡ ያጠራቀሙት ፡ ጥቂት ፡
ገንዘብ ፡ ይሻላል ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩፤ የምትሞቱበትን ፡ ቀን ፡ አስቡ ፡ ነፍሳችሁ ፡
ከሥጋችሁ ፡ በተለየች ፡ ጊዜ ፡ ገንዘባችሁንም ፡
ለሌላ ፡ በተዋችሁ ፡ ጊዜ ፡ ወደማታውቁት ፡ ጐዳ
ናም ፡ በሄዳችሁ ፡ ጊዜ ፡ የምትመጣባችሁን ፡
መከራ ፡ አስቧት ።
፪፤ የሚቀበሏችሁ ፡ አጋንንትም ፡ ክፉዎች ፡ ናቸው ፡
መልካቸውም ፡ ጥቁ ፡ ነው ፡ በግርማቸውም ፡
የሚያስፈሩ ፡ ናቸው ፡ ቃላችሁን ፡ አይሰሙም ፡
ቃላቸውንም ፡ አትሰሙም ።
፫፤ የፈጣሪያችሁ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ፈቃድ ፡ ስለ ፡
አላደረጋችሁ ፡ በስመናችኋቸውም ፡ ጊዜ ፡ ልመ
ናችሁን ፡ አይሰሟችሁም ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ፈጽ
መው ፡ ያስፈሯችኋል ።

አጋንንት ፡ ይፈሯቸዋልና ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ፬፤
ፈቃድ ፡ በፈጸሙ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ፍርሃት ፡ የለ
ባቸውም ። በኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ ነፍሶች ፡
ግን ፡ አጋንንት ፡ ይዘባበቱባቸዋል ።
ይህን ፡ ዓለም ፡ ስለ ፡ ናቁት ፡ ፈጽሞ ፡ ደስ ፡ ያሰ ፭፤
ኛቸዋልና ፡ የደጋጎች ፡ ሰዎች ፡ ነፍሳት ፡ ግን ፡
በመላእክት ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፡
የኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ ነፍሳትን ፡ ግን ፡ ክፉ
ዎች ፡ የሆኑ ፡ መላእክት ፡ ይቀበሏቸዋል ።
የጻድቃንን ፡ ነፍሳት ፡ ያረጋጋቸው ፡ ዘንድ ፡ ከእ ፮፤
ግዚአብሔር ፡ ይላክሉና ፡ የደጋጎች ፡ ሰዎችን ፡
የጻድቃንን ፡ ነፍሳት ፡ የይቅርታ ፡ መላእክት ፡
ይቀበሏቸዋል ፡ በኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ ነፍ
ሶች ፡ ይዘባበቱባቸው ፡ ዘንድ ፡ ክፉዎች ፡ የሆኑ ፡
መላእክት ፡ ከዲያብሎስ ፡ ይላካሉና ፡ የኃጢአ
ተኞች ፡ ሰዎች ፡ ነፍሶችን ፡ አጋንንት ፡ ይቀበ
ሏቸዋል ።
ኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ ወዮላችሁ ፡ የምትሞቱ ፯፤
በት ፡ ቀን ፡ ሳትደርስባችሁ ፡ ለራሳችሁ ፡ አል
ቅሱ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ በደረሳችሁ ፡ ጊዜ ።
ያለ ፡ መከራና ፡ ያለ ፡ ደዌ ፡ በተድላና ፡ በደስታ ፡ ፰፤
ትኖሩ ፡ ዘንድ ፡ ዘመናችሁ ፡ ሳያልፍ ፡ ባለ ፡ ዘመ
ናችሁ ፡ ንስሐ ፡ ግቡ ፡ እንጂ ፡ ከሞታችሁ ፡ በኋላ ፡
ያለፈው ፡ ዘመናችሁ ፡ አይመለስምና ፡ አልቅሱ ።
ከእግዚአብሔር ፡ ወደሚያርቅ ፡ ወደ ፡ ከንቱ ፡ ፱፤
ፈቃድ ፡ እንዳይሆንባችሁ ፡ በናንተ ፡ ጽኑ ፡ ነቀፋ ፡
መቀማጠል ፡ መብልንና ፡ ተድላን ፡ ደስታንም ፡
መውደድ ፡ በናንተ ፡ አይገኝ ፡ ያለልክ ፡ የጠገ
በች ፡ ሰውነት ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ አታ
ስብምና ፡ የዲያብሎስ ፡ ሀብት ፡ ያድርብታል ፡
እንጂ ፡ በዚ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ አያድርበትምና ፡
ተድላ ፡ ደስታውን ፡ መውደድ ፡ በናንተ ፡ አይ
ገኝ ።
ሙሴ ፡ ያዕቆብ ፡ በልቶ ፡ ጠገበ ፡ ወፈረ ፡ ረዘመ ፡ ፲፤
ሰፋ ፡ የፈጠረው ፡ እግዚአብሔርም ፡ ተለየው ።
አንዋወሩም ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ራቀ ፡ ብሎ ፡ ፲፩፤
ሙሴ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ ያለልክ ፡ ያለመጠን ፡
የጠገበች ፡ ሰውነት ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡
አታስብምና ፡ ተድላ ፡ ደስታን ፡ መውደድ ፡
በናንተ ፡ ዘንድ ፡ አይገኝ ፡ ያለልክ ፡ የሆድ ፡
ጥጋብ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ እንዳለ ፡ እሪያና ፡ እን
ዳለሴ ፡ ፈረስ ፡ መሆን ፡ ነውና ፡ ያለልክ ፡ መጠጣ
ትና ፡ መብላት ፡ ዝሙትም ፡ በእናንተ ፡ አይገኝ ።
በልክ ፡ የሚበላ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፲፪፤
ረድኤት ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፡ እንደ ፡ አድማስም ፡
ደንጊያ ፡ አጥርም ፡ እንዳለው ፡ ግምብ ፡ ጸንቶ ፡
ይኖራል ፤ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ የዘነጋ ፡
ሰው ፡ የሚያበርረው ፡ ሳይኖር ፡ ይሸሻል ።
ደግ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ በመፈራት ፡ ይኖ ፲፫፤
ራል ።
እግዚአብሔርን ፡ የማይወዱ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ፲፬፤
ሕጉን ፡ አይጠብቁም ፡ ልቡናቸውም ፡ የቀና ፡
አይደለም ።
እግዚአብሔርም ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሳሉ ፡ ጎዘ ፲፭፤

ንና ፡ ድንጋጼ ፡ የመጣበቸዋል ፡ በመንቀጥቀጥና ፡
በፍርሃት ፡ ተይዘው ፡ ገንዘባቸውን ፡ በመነጠቅ ፡
ቁጥርም ፡ በሌለው ፡ መከራ ፡ ተይዘው ፡ ከጌቶ
ቻቸው ፡ እጅ ፡ እጃቸውን ፡ በሰንሰለት ፡ ታሥ
ረው ።
፲፯ ከመከራውም ፡ ያረፉ ፡ እንዳይሆኑ ፡ አነዋወራ
ቸውም ፡ በተድላ ፡ በደስታ ፡ እንዳይሆን ፡ እየ
ራሳቸው ፡ በሆኑ ፡ በሚያስደነግጡ ፡ መከራዎች ፡
ሳሉ ፡ እንዳያርፉ ፡ ኀዘንና ፡ ድንጋጤውን ፡ ያመ
ጣበቸዋል ።

ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩ ዳዊት ፡ በእግዚአብሔር ፡ አመንኩ ፡ አልፈ
ራም ፡ ሰው ፡ ምን ፡ ያደርገኝ ፡ ብዬ ፡ ብሎ ፡ እንደ ፡
ተናገረ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ባመኑ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡
ፍርሃትና ፡ ድንጋጼ ፡ የሌባቸውም ።
፪ ዳግመኛም ፡ አርበኞች ፡ ቢከቡኝ ፡ እኔ ፡ በሱ ፡
አመንሁ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አንዲት ፡ ነገር ፡
ለመንሁት ፡ ያቺኑ ፡ እፈልጋለሁ ፡ ብሎ ፡ እንደ ፡
ተናገረ ፡ በሱ ፡ ያመኑ ፡ ሰዎች ፡ ፍራት ፡ የለባቸ
ውም ፡ በሱ ፡ ያመነ ፡ ሰው ፡ ለዘላለሙ ፡ በሕይ
ወት ፡ ይኖራል ፡ ከክፉ ፡ ነገርም ፡ የተነሣ ፡ አይ
ፈራም ።
፫ በእግዚአብሔር ፡ አምኖ ፡ ያፈረ ፡ ሰው ፡ ማነው ፡
ለምኖትስ ፡ ቸል ፡ ያለው ፡ ማነው ።
፬ የወደደኝን ፡ እወደዋለሁ ፡ ያከበረኝንም ፡ አከብ
ረዋለሁ ፡ በንስሐ ፡ ወደኔ ፡ የተመለሰውን ፡ እጠ
ብቀዋለሁ ፡ ብሏልና ፡ እሱን ፡ አምኖ ፡ ያፈረ ፡
ሰው ፡ ማነው ።
፭ እውነት ፡ ፈርዳችሁ ፡ የበልቱቱን ፡ ሰውነት ፡
አድኑ ፡ በክፉ ፡ ነገር ፡ ከሚቃወማችሁ ፡ ሁሉ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ያድናችሁ ፡ ዘንድ ፡ አድኗቸው ፡
ጠብቋቸው ፡ የደጋግ ፡ ሰዎች ፡ ልጆች ፡ ይከብራ
ሉና ፡ አትርፈው ፡ ይሰጣሉ ፡ እንጂ ፡ እህልንም ፡
አይቸገሩምና ፡ ከናንተም ፡ በኋላ ፡ ልጆቻችሁን ፡
ያድናቸዋል ።

ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩ ኢዮብ ፡ በእግዚአብሔር ፡ አመነ ፡ ፈጣሪው ፡
እግዚአብሔርን ፡ ማመስገንን ፡ ቸል ፡ አላለምና ፡
እግዚአብሔር ፡ የአዳም ፡ ልጆች ፡ ጠላት ፡ ዲያ
ብሎስ ፡ ካመጣበት ፡ መከራ ፡ ሁሉ ፡ አዳነው ፡
እግዚአብሔር ፡ ሰጠ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነሳ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ በኔ ፡ እንደ ፡ ወደደ ፡ ሆነ ፡ በሁሉም ፡
በምድርና ፡ በሰማይ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ስሙ ፡
የተመሰገነ ፡ ይሁን ፡ አለ ፡ እንጂ ፡ ልቡናውን ፡
አላሳዘነምና ፡ አዳነው ።
፪ እግዚአብሔርም ፡ ኢዮብን ፡ ልቡ ፡ ከኀጢአት ፡
እንደነጻች ፡ ባየው ፡ ጊዜ ፡ በብዙ ፡ ክብር ፡ ተቀ
በለው ።
፫ ከቀደመ ፡ ገንዘቡ ፡ ይልቅ ፡ የሚበዛ ፡ ገንዘብንም ፡
ሰጠው ፡ ፈጽሞ ፡ መከራውን ፡ ታግሷልና ፡ የደ
ረሰበትን ፡ መከራ ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ መታገሡ ፡
ከቍስሉም ፡ ፈወሰው ።
ወደናንተ ፡ ከሚላኩ ፡ አጋንንት ፡ የተነሣ ፡ እና ፬
ንተም ፡ እንደሱ ፡ መከራውን ፡ ብትታገሡ ፡
የተደነቃችሁ ፡ ትሆናላችሁ ።
መከራውን ፡ ታገሡ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከሚጠሏ ፭
ችሁ ፡ ሰዎች ፡ አምባ ፡ መጠጊያ ፡ ይሆናችሁ ፡
ዘንድ ፡ ከናንተም ፡ በኋላ ፡ ለልጅ ፡ ልጆቻችሁና ፡
ለልጆቻችሁም ፡ አምባ ፡ መጠጊያ ፡ ይሆናቸው ፡
ዘንድ ፡ ከመጣባችሁ ፡ መከራ ፡ የተነሣ ፡ ልቡና
ችሁን ፡ አታሳዝኑ ፡ እመኑት ፡ እሱም ፡ አምባ ፡
መጠጊያ ፡ ይሆናችኋል ።
ለምኑት ፡ ይሰማችኋል ፡ ተከሩ ፡ አድርጉ ፡ ፮
እሱም ፡ ይቅር ፡ ይላችኋል ፡ ለምኑት ፡ እሱም ፡
አባት ፡ ይሆናችኋል ።
መርዶክዮስንና ፡ አስቴርን ፡ ዮዲትን ፡ ጌዴዎን ፯
ንም ፡ ዲቦራና ፡ ባርቅንም ፡ ዮፍታሔንና ፡ ሰም
ሶምንንም ።
በእግዚአብሔር ፡ ለማመን ፡ የጨከኑ ፡ ጠላቶቻ ፰
ቸውም ፡ ድል ፡ ያልነሣቸው ፡ እንደነሳቸው ፡
ያሉ ፡ ሌሎች ፡ ሰዎችንም ፡ አስቡ ።
እግዚአብሔር ፡ እውነተኛ ፡ ነውና ፡ ፊት ፡ አይቶ ፡ ፱
አያደላምና ፡ በራሳቸው ፡ ኀጢአት ፡ ይሠሩ ፡
ዘንድ ፡ የሚወዱ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ፍዳን ፡ ተቀበሉ ፡
የሚፈሩትን ፡ ሕጉንም ፡ የሚጠብቁ ፡ ሰዎችን ፡
ሁሉ ፡ ሰውነት ፡ ይጠብቃል ፡ መወደድንና ፡ ክብ
ርንም ፡ ይሰጣቸዋል ።
በመውጣታቸውና ፡ በመግባታቸው ፡ በሕይወ ፲
ታቸውና ፡ በሞታቸው ፡ በመነሣታቸውና ፡ በመ
ቀመጣቸውም ፡ ደስ ፡ ያሰኛቸዋል ፡ እሱ ፡ ያድ
ናል ፡ ይገላልና ።
እሱ ፡ ያሳዝናል ፡ ይቅር ፡ ይላልና ። ፲፩
እሱ ፡ ያደኸያል ፡ ያከብራልና ፡ እሱ ፡ ያጐስቍ ፲፪
ላል ፡ ያከብራልና ፡ ደስ ፡ ያሰኛቸዋል ።

ምዕራፍ ፡ ፱ ።

በሰማይም ፡ ያለ ፡ ቢሆን ፡ በምድርም ፡ ያለ ፡ ፩
ቢሆን ፡ ረቂቅም ፡ ግዙፍም ፡ ቢሆን ፡ ሁሉም ፡
የሱ ፡ ገንዘብ ፡ ሁሉም ፡ በሥራቱ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖ
ራል ።
ዓለሙን ፡ ሁሉ ፡ ከፈጠረ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ፪
ከሕጉ ፡ ከሥራቱ ፡ የወጣ ፡ የለም ፡ በሰማይ ፡
የሚበር ፡ ያሞራ ፡ ፍሊጋ ፡ ቢሆን ፡ ወደ ፡ ወደደ
በት ፡ መሄጃውን ፡ እሱ ፡ ያዛል ።
በዋሻ ፡ የሚኖር ፡ የምድር ፡ እባብንም ፡ ጐዳና ፡ ፫
ወደ ፡ ወደደበት ፡ እሱ ፡ ያዛል ፡ በባሕር ፡ ላይ ፡
የሚሄድ ፡ የመርከብን ፡ ጐዳና ፡ ከእግዚአብ
ሔር ፡ ብቻ ፡ በቀር ፡ ጐዳናውን ፡ የሚያውቀው ፡
የለም ።
የጻድቅም ፡ የኃጥእም ፡ ነፍስ ፡ ብትሆን ፡ ከሥ ፬
ጋዋ ፡ በተለየች ፡ ጊዜ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ብቻ ፡
በቀር ፡ ነፍስ ፡ የምትሄድበትን ፡ ጐዳና ፡ የሚያ
ውቅ ፡ የለም ።
በምድረ ፡ በዳ ፡ በተራራም ፡ ትዝር ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ፭
የምትዘርበትን ፡ ማን ፡ ያውቃል ፡ እንደ ፡ ወፍም ፡
ትበር ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በተራራ ፡ ላይ ፡ እንደሚወ

ርድ ፡ እንደ ፡ ሰማይ ፡ ጠል ፡ ትሆን ፡ እንደ ፡ ሆነ ።
፮ እንደ ፡ ጥልቅ ፡ ነፋስም ፡ ትሆን ፡ እንደሆን ፡
ጐዳናውን ፡ እንደሚያቀና ፡ እንደ ፡ መብረቅም ፡
ትሆን ፡ እንደ ፡ ሆነ ።
፯ በጥልቁ ፡ መካከል ፡ እንደሚያበሩ ፡ ከዋክብ
ትም ፡ ትሆን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በጥልቁ ፡ መካከል ፡
እንደሚከመር ፡ በበሕርም ፡ ዳር ፡ እንዳለ ፡ አሸዋ ፡
ትሆን ፡ እንደ ፡ ሆነ ።
፰ በባሕሩም ፡ ጥልቅ ፡ ዳርቻ ፡ እንደ ፡ ጸና ፡ እንደ ፡
አድማስ ፡ ደንጊያም ፡ ትሆን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
በውኃ ፡ መፍሰሻ ፡ እንደ ፡ በቀለች ፡ ያማረ ፡ ፍሬ
ዋንም ፡ እንደምትሰጥ ፡ እንደ ፡ እንጨትም ፡
ትሆን ፡ እንደ ፡ ሆነ ።
፱ ዋዕየ ፡ ፀሐይ ፡ እንደሚያቃጥለው ፡ ነፋስም ፡
አንሥቶ ፡ ወዳልበቀለበት ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ በታ ፡
እንደሚወስደው ፡ ፍለጋውም ፡ እንደማይገኝ ፡
እንደ ፡ መቃ ፡ መስዩም ፡ ትሆን ፡ እንደ ፡ ሆነ ።
፲ ፍለጋው ፡ እንደማይገኝ ፡ እንደ ፡ ጉም ፡ ሽን
ትም ፡ ትሆን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ሥራ ፡ ማን ፡ ያውቃል ፡ መከሮቹ ፡ እነማናቸው ፡
ከማንስ ፡ ጋራ ፡ መከረ ።
፲፩ የእግዚአብሔር ፡ አሳቡ ፡ ከሰው ፡ የተሠወረ ፡
ነውና ፡ ሥራውን ፡ ማን ፡ መርምሮ ፡ ያውቃል ።
፲፪ እሱ ፡ ምድርን ፡ በውሀ ፡ ላይ ፡ ፈጥሯታልና ፡
ያለ ፡ ካስማም ፡ አጥንቷታልና ፡ የእግዚአብሔ
ርን ፡ ምክሩንና ፡ ጥበቡን ፡ መርምሮ ፡ የሚያ
ውቅ ፡ የለም ፡ በፍጹም ፡ ጥበቡም ፡ ሰማይን ፡
ፈጠረው ፡ በነፋስም ፡ አጸናው ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ጠፈ
ርንም ፡ እንደ ፡ ድንኳን ፡ ዘረጋው ።
፲፫ በምድር ፡ ላይ ፡ ዝናምን ፡ ያዘንሙ ፡ ዘንድ ፡ ደመ
ናትን ፡ አዘዛቸው ፡ ሣርንም ፡ ያበቅላል ፡ በእግ
ዚአብሔር ፡ አምነን ፡ አንድነት ፡ ደስ ፡ ይለን ፡
ዘንድ ፡ ለሰው ፡ ምግብ ፡ ሊሆኑ ፡ ቍርጥ ፡ የሌላ
ቸው ፡ ፍሬዎችንም ፡ ያበቅላል ።
፲፬ ተድላውን ፡ ደስታውንና ፡ ድልቡን ፡ ሁሉ ፡ ጽጋ
ቡንም ፡ ለአዳም ፡ ልጆች ፡ የሚሰጥ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ነው ፡ ከምድር ፡ ፍሬ ፡ የሰጣቸውን ።
፲፭ ያማረ ፡ መጐናጸፊያንም ፡ ያለበሳቸውን ፡ የሚ
ወደደውን ፡ በረከት ፡ ሁሉ ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ፈቃድ ፡ ለሚፈጽሙ ፡ ሰዎች ፡ የተሰጠ ፡ ደስታ
ውንና ፡ ተድላውን ፡ የሰጣቸው ፡ እግዚአብሔ
ርን ፡ ጠግበው ፡ ያመሰግኑት ፡ ዘንድ ፡ የሚሰጥ ፡
እግዚአብሔር ፡ ነው ።
፲፮ የእግዚአብሔርን ፡ ሕጉን ፡ ለሚጠብቁ ፡ ላበቶ
ቻቸው ፡ በዘጋጀው ፡ ቤት ፡ በመንግሥት ፡ ሰማ
ይም ፡ መወደድንና ፡ ክብርን ፡ ይሰጣቸዋል ።
፲፯ በአምልኮቱና ፡ በሕጉም ፡ ፀንተው ፡ ለኖሩ ፡
ከሕጉም ፡ ላልወጡ ፡ ለተከባከባቸው ፡ ለመገበ
ቸው ፡ ሥራቱንና ፡ ሕጉን ፡ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ፡
ላገነናቸው ፡ ላሰደጋቸው ፡ ላበቶቻቸው ፡ በዘጋ
ጀው ፡ በታ ፡ በመንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ መወደድ
ንና ፡ ክብርን ፡ ይሰጣቸዋል ፡ እኔም ፡ ጠላታቻ
ውን ፡ በማድከም ፡ ሰውነታቸውንም ፡ በመጠ
በቅ ፡ እግዚአብሔር ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ለወዳጆቹ ፡
የሚያደርገውን ፡ አየሁ ።
የለመኑትን ፡ ሁሉ ፡ እንዲሰጣቸው ፡ ፈቃዳቸ ፲፰
ውንም ፡ እንዲፈጽምላቸው ፡ አየሁ ፡ ከእግዚ
አብሔር ፡ ትእዛዝ ፡ አትወጡ ፡ የእግዚአብሔ
ርንም ፡ ፈቃድ ፡ ፈጽሙ ።
እንዳይቈጣባችሁ ፡ አንድ ፡ ጊዜም ፡ እንዳያጠ ፲፱
ፋችሁ ፡ ቀድሞ ፡ ከኖራችሁበት ፡ ተቈጥቶም ፡
በመከራው ፡ እንዳይገርፋችሁ ፡ ቀድሞ ፡ ከነበ
ራችሁበት ፡ ከበቶቻችሁ ፡ ሥራት ፡ እንዳት
ወጡ ፡ ማደሪያችሁም ፡ እስከ ፡ ዘላለሙ ፡ ድረስ ፡
መውጫ ፡ በሌለበት ፡ በገሃነም ፡ እንዳይሆን ፡
ከትእዛዙና ፡ ከሕጉ ፡ አትውጡ ።
በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በቆማችሁ ፡ ጊዜ ፡ በጎ ፡ ፳
ሥራ ፡ ያደርግላችሁ ፡ ዘንድ ፡ ነፍሳችሁ ፡ ከሥ
ጋችሁ ፡ ስትለይ ፡ የፈጣሪያችሁ ፡ የእግዚአብሔ
ርን ፡ ሕግ ፡ ጠብቁ ።
የምድርና ፡ የሰማይ ፡ መንግሥት ፡ ለሱ ፡ ነውና ፡ ፳፩
መንግሥትና ፡ ከሃሊነትም ፡ ለሱ ፡ ነውና ፡ መሪ
ራትና ፡ ይቅር ፡ ማለትም ፡ ለሱ ፡ ብቻ ፡ ነውና ።
እሱ ፡ ባለ ፡ ጸጋ ፡ ያደርጋል ፡ ያደኸያልና ፡ ያገሎሳ ፳፪
ቊላል ፡ ያከብራልና ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡
ጠብቁ ።
ዳዊትም ፡ ሰው ፡ ከንቱን ፡ ይመስላል ፡ ዘመኑም ፡ ፳፫
እንደ ፡ ጥላ ፡ ያልፋል ፡ እያለ ፡ ስለሱ ፡ ተናገረ ።
አቤቱ ፡ አንተ ፡ ግን ፡ ለዘላለም ፡ ትኖራለህ ፡ ስም ፡ ፳፬
አጠራርህም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ስለሱ ፡
ተናገረ ።
ዳግመኛም ፡ መንግሥትህ ፡ የዓለሙ ፡ ሁሉ ፡ ፳፭
መንግሥት ፡ ነው ፡ አገዛዝህም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡
ነው ፡ አለ ፡ ከሳኦል ፡ አምጥተህ ፡ መንግሥትን ፡
ለዳዊት ፡ መለስህ ።
አንተን ፡ ግን ፡ የሚሾምህ ፡ የለም ፡ አንተንም ፡ ፳፮
መሻር ፡ የሚችል ፡ የለም ፡ አንተ ፡ ሁሉን ፡ ታያ
ለህ ፡ እንጂ ፡ አንተን ፡ ማየት ፡ የሚችል ፡ የለም ።
መንግሥትህም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ለዘላለሙ ፡ አይ ፳፯
ጠፋም ፡ እሱን ፡ የሚገዛው ፡ የለም ፡ እሱ ፡ ግን ፡
ሁሉን ፡ ይገዛል ፡ ሁሉን ፡ ያያል ፡ እሱን ፡ ግን ፡
የሚያየው ፡ የለም ።
ያመሰግኑት ፡ ዘንድ ፡ ያለጥርጥር ፡ በቀና ፡ ልቡና ፡ ፳፰
አምልኮቱንም ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ፡ እሱ ፡ ሰውን ፡
በመልኩ ፡ በምሳሌው ፡ ፈጥሮታልና ፡ ኩላሊት ፡
ያጤሰውን ፡ ልቡና ፡ ያመላለሰውን ፡ መርምሮ ፡
ያውቃል ፡ ለፈጠራቸው ፡ ለመገባቸው ፡ ላሳደ
ጋቸው ፡ ላገነናቸው ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ብቻ ፡
ነው ፡ እንጂ ፡ ለልዩ ፡ ጣዖቶችም ፡ የሚሰግዱ ፡
እንዳይሆኑ ፡ እሱ ፡ በመልኩ ፡ በምሳሌው ፡ ፈጥ
ሮታልና ፡ ኩላሊት ፡ ያጤሰውን ፡ ልቡና ፡ ያመ
ላለሰውን ፡ መርምሮ ፡ ያውቃል ።
ለድንጋይ ፡ ለእንጨት ፡ የሰው ፡ እጅ ፡ ለሠራ ፳፱
ቸው ፡ ለብርና ፡ ለወርቅም ፡ ይሰግዳሉ ፡ እንጂ ።
ኃጢአታቸው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ጸንቶ ፡ ፴
ይኖር ፡ ዘንድ ፡ የመሥዋዕታቸው ፡ ጢስ ፡ ወደ ፡
ሰማይ ፡ እስኪወጣ ፡ ድረስ ፡ መሥዋዕትም ፡
ይሠዉላቸዋል ፡ እንጂ ፡ እነሳቸው ፡ ግን ፡ የፊ

ጠራቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ማምለክ ፡ እምቢ ፡
እሉ ፡ ጣዖታቸውን ፡ በማምለክ ፡ ስለ ፡ ሠሩት ፡
ኃጢአታቸው ፡ ሁሉ ፡ ይከሰቸዋል ።
፴፩፤ ለጣዖት ፡ መስገድን ፡ የሚገባ ፡ ያይደለ ፡ አደ
ራኛ ፡ ሥራንም ፡ ሁሉ ፡ በክክብ ፡ ማሚረትን ፡
ጥንቈላን ፡ ጣዖት ፡ ማምለክን ፡ ክፉ ፡ ሬቀድን ፡
እግዚአብሔር ፡ የማይወደውንም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡
ተማሩ ፡ እንጂ ፡ የተማሩትን ፡ የእግዚአብሔ
ርን ፡ ትእዛዝ ፡ አልጠበቁም ።
፴፪፤ በገልጋዮቹ ፡ በመላእክትና ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ በሚመሰገኑ ፡ ገንዘብ ፡ ከኃጢአትና ፡ ከበ
ደል ፡ ሰውነታቸውን ፡ ያድኑ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአ
ብሔርን ፡ ማመስገን ፡ አልወደዱምና ፡ በጎ ፡
ሥራ ፡ በማጣት ፡ ይኸን ፡ ሁሉ ፡ ይሠራሉ ።
፴፫፤ ከተቀበሩበት ፡ ሰውነቶቻቸውም ፡ ከጠፉበት ፡
ከመቃብር ፡ ሁሉም ፡ አንድነት ፡ በተነሡ ፡
ጊዜ ፡ ነፍሳቸው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ባዶ
ዋን ፡ ትቆማለች ፡ ነፍሳቸውም ፡ ለደጋጎች ፡
ሰዎች ፡ በተዘጋጀች ፡ በመንግሥተ ፡ ሰማይ ፡
ኖረች ።
፴፬፤ የኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ ነፍስ ፡ ግን ፡ በገሃ
ነም ፡ ትኖራለች ፡ መቃብራትም ፡ በተከፈቱ ፡
ጊዜ ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ ይነሣሉ ፡ ነፍሳትም ፡
ቀድሞ ፡ ወደ ፡ ተለዩዋቸው ፡ ወደ ፡ ሥጋት ፡
ይመለሳሉ ።
፴፭፤ ከናታቸው ፡ ሆድ ፡ ዕራቁታቸውን ፡ እንደተወ
ለዱ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ዕራቁታቸውን ፡
ይቆማሉ ፡ ከሕፃንነት ፡ ጀምሮ ፡ እስከዚያን ፡
ጊዜ ፡ የሠሩት ፡ ኃጢአታቸውም ፡ ይገለጣል ።
፴፮፤ የኃጢአታቸውን ፡ ፍዳ ፡ በሰውነታቸው ፡ ይቀ
በላሉ ፡ ጥቂትም ፡ ብዙም ፡ ኃጢአት ፡ ቢሠሩ ፡
እንደ ፡ ኃጢአታቸው ፡ ፍዳቸውን ፡ ይቀበላሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩፤ ቀድሞ ፡ እንዳደረበቻው ፡ ከእግዚአብሔር ፡
የሚገኝ ፡ ደመ ፡ ነፍሱ ፡ ያድርባቸዋልና ፡ የሞቱ ፡
ሰዎችንም ፡ መነሣት ፡ ከላመንክ ፡ ከናት ፡ ከበኋ
ቸው ፡ ሳይወለዱ ፡ ፍጥረቶች ፡ በክረምት ፡ እን
ዲነሡ ፡ ስማ ።
፪፤ እንዲሞቱም ፡ ቀድሞ ፡ በቃሉ ፡ ያዛቸዋል ።
፫፤ ሥጋቸው ፡ ፈርሶ ፡ በስብሶ ፡ ዳግመኛ ፡ ታድሶ ፡
እሱ ፡ እንደ ፡ ወደደ ፡ ይነሣሉ ።
፬፤ ዳግመኛም ፡ ዝናም ፡ በወረደ ፡ ጊዜ ፡ ምድር
ንም ፡ በጠገበት ፡ ጊዜ ፡ ቀድሞ ፡ እንደ ፡ ተፈ
ጠሩ ፡ ተነሥተው ፡ ይኖራሉ ።
፭፤ በደማዊት ፡ ነፍስ ፡ ሕያው ፡ የሚሆኑት ፡ በዚህ ፡
ዓለም ፡ የሚኖሩት ፡ ውሀም ፡ የሚያስገኛቸው ፡
ይፈጠሩ ፡ ብሎ ፡ ተፈጥረዋልና ፡ የእግዚአብ
ሔር ፡ ሥልጣኑም ፡ በውሀው ፡ ላይ ፡ ያድራልና ፡
በሥልጣኑ ፡ በቃሉ ፡ ደማዊት ፡ ነፍስ ፡ ትሰ
ጣቸዋለች ።
፮፤ በሥልጣኑ ፡ በቃሉ ፡ ያለ ፡ አባትና ፡ ያለ ፡ እናት ፡
ይፈጠራሉና ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ አይነሡም ፡ የም
ትል ፡ አንተ ፡ ዕውረ ፡ ልቡና ፡ እውቀት ፡ ጥበብ ፡
ከሌህ ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ በፈጣሪያቸው ፡ በእግ
ዚአብሔር ፡ ቃል ፡ እንደምት ፡ አይነሡም ፡ ትላ
ለህ ።
በመቃብር ፡ አመድ ፡ ትቢያ ፡ የሆኑ ፡ የሞቱ ፡ ፯፤
ሰዎች ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ይነሣሉና ፡
አንተስ ፡ ንስሐ ፡ ግባ ፡ ወደ ፡ ሃይማኖትህም ፡
ተመለስ ።
ቀድሞ ፡ ቃሉ ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ ከእግዚአብ ፰፤
ሔር ፡ በተገኘ ፡ በይቅርታው ፡ ጠል ፡ ይነሣሉ ፡
ያም ፡ ቃል ፡ ዓለሙን ፡ ሁሉ ፡ ዘሮ ፡ የሞቱትን ፡
ሰዎች ፡ እንደወደደ ፡ ያስነሣቸዋል ።
ተነሥተህም ፡ በፊቱ ፡ እንድትቆም ፡ እወቅ ፡ ፱፤
በልቡናህም ፡ ድንቍርና ፡ በመቃብር ፡ የምት
ቀር ፡ አይምሰልህ ።
እንዲህ ፡ አይደለም ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ እንደ ፡ ፲፤
ሠራኸው ፡ ሥራ ፡ መጠን ፡ በጎም ፡ ቢሆን ፡
ክፉም ፡ ቢሆን ፡ ተነሥተህ ፡ ፍዳህን ፡ ትቀበላ
ለህ ፡ እንጂ ፡ የምትቀር ፡ አይምሰልህ ፡ ይህች ፡
ቀን ፡ ፍዳ ፡ የሚቀበሉባት ፡ ቀን ፡ ናትና ።
በትንሣኤም ፡ ጊዜ ፡ በሠራኸው ፡ ኃጢአትህ ፡ ፲፩፤
ሁሉ ፡ ፍዳህን ፡ ትቀበላለህ ፡ ከሕፃንነትህ ፡ ጀምሮ ፡
እስከዚያን ፡ ጊዜ ፡ ድረስ ፡ የተጻፈ ፡ የኃጢአት
ህን ፡ ፍዳ ፡ ትጨርሳለህ ፡ ኃጢአትህንም ፡ ትክድ ፡
ዘንድ ፡ እንደዚህ ፡ ዓለም ፡ ሥራ ፡ በኃጢአትህ ፡
የምታመካኘው ፡ ምክንያት ፡ የለህም ።
ሐሰተኛ ፡ ቃልህን ፡ በፊትህ ፡ እውነት ፡ እንደ ፲፪፤
ምታደርገው ፡ የተናገርኸው ፡ አሰቱንም ፡ ነገር ፡
እውነት ፡ እንደምታደርገው ፡ እንደዚህ ፡ ዓለም ፡
ሥራ ፡ የምታመካኘው ፡ ምክንያት ፡ የለህም ።
እሱ ፡ የሠራኸውን ፡ ክፉ ፡ ሥራህን ፡ ሁሉ ፡ የም ፲፫፤
ታውቅበህ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ በፈጣሪዋ ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ ፊትም ፡ የምትገልጥበህ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የእ
ግዚአብሔር ፡ ቃሉ ፡ በንተ ፡ አድሮ ፡ ይናገርብ
ሃልና ፡ በምታመካኘው ፡ ምክንያት ፡ የለህም ።
ስለ ፡ ሠራኸው ፡ ኃጢአትህ ፡ በዚያ ፡ ታፍራለህ ፡ ፲፬፤
በማረ ፡ ሥራቸው ፡ ከሚመሰገኑ ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡
ትመሰገን ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ፍርድ ፡ በሚ
ፈረድበት ፡ ቀን ፡ በሰውና ፡ በመላእክት ፡ ፊት ፡
እንዳታፍር ፡ ወደዚያ ፡ ሳትደርስ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡
ፈጥነህ ፡ ንስሐ ፡ ግባ ።
ከመላእክት ፡ ጋራ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚያ ፲፭፤
መሰግኑ ፡ ሰዎች ፡ ሳያፍሩ ፡ ከፈጣሪያቸው ፡
ዋጋቸውን ፡ ይቀበላሉ ፡ በመንግሥተ ፡ ሰማ
ይም ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፡ ነገር ፡ ግን ፡ በሥጋህ ፡
በሕይወት ፡ ሳለህ ፡ በጎ ፡ ሥራን ፡ ካልሠራህ ፡ ከጻ
ድቃን ፡ ጋራ ፡ እድል ፡ የለህም ።
ዕውቀት ፡ ሳለህ ፡ ንስሐ ፡ የምትገባበት ፡ ይህ ፡ ፲፮፤
ዓለምም ፡ ሳለህ ፡ አልተዘጋጀህምና ፡ የማይረብ ፡
ጸጸት ፡ ይሆንብሃል ፡ ገንዘብም ፡ ሳለህ ፡ የተራብ
ውን ፡ አላጕረስኸውምና ።
ልብስም ፡ ሳለህ ፡ የተራቈተውን ፡ አላለበስከው ፲፯፤
ምና ፡ ሥልጣንም ፡ ሳለህ ፡ የተበደለውን ፡ አላ
ዳንከውምና ።
ተመልሰ ፡ ንስሐ ፡ ይገባ ፡ ዘንድ ፡ ቀድሞ ፡ በለ ፲፰፤

ማወቅ ፡ የሠራውንም ፡ ኃጢአቱን ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ይቅር ፡ ይለው ፡ ዘንድ ፡ እውቀት ፡ ሳለህ ፡
ኃጥኡን ፡ ሰው ፡ አላስተማርከውምና ፡ ድል ፡
መንሳትን ፡ ትችል ፡ ዘንድ ፡ ኃይል ፡ ሳለህ ፡ ከሚ
ጣሉህ ፡ ከአጋንንትም ፡ ጋራ ፡ አልተዋጋህምና ።
፲፱ በሥጋ ፡ ያለ ፡ የሕፃንነትህን ፡ ኃይል ፡ ታደክም ፡
ዘንድ ፡ ጽናትም ፡ ሳለህ ፡ አልጾምህም ፡ አልጸ
ለይህምና ፡ በዓለም ፡ ያለ ፡ በሥጋ ፡ ማድላት ፡
ያይደለ ፡ ለጽድቅም ፡ ራስህን ፡ ታስገዛ ፡ ዘንድ ።
፳ ባማረ ፡ መጠጥና ፡ በጣፈጠ ፡ መብል ፡ በዚህ ፡
ዓለም ፡ ሳለ ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ማድላት ፡ ያይደለ ፡
በቀጭን ፡ ልብስም ፡ በብርና ፡ በወርቅም ፡ ማጌጥ ፡
ያይደለ ።
፳፩ የከበሩ ፡ በሆኑ ፡ መረግድና ፡ ጳዝዮን ፡ በሚባሉ ፡
በሕንደኬ ፡ ዕንቈች ፡ ማጌጥ ፡ ያይደለ ፡ ራስህ
ንም ፡ ለጽድቅ ፡ ታስገዛ ፡ ዘንድ ፡ ጽናትም ፡
ሳለህ ፡ አልጾምክም ፡ አልጸለይክምና ፡ የማይ
ረባ ፡ ጸጸት ፡ ይሆንብሃል ፡ ይህ ፡ የሚገባ ፡ የሰው ፡
ጌጥ ፡ አይደለም ።
፳፪ ለሰው ፡ ጌጡስ ፡ ንጽሕና ፡ ጥበብ ፡ ዕውቀት ፡ ያለ
መቃናት ፡ ያለ ፡ ምቀኝነት ፡ ያለ ፡ መጠራጠር ፡
ያለ ፡ ጸብ ፡ በሚገባ ፡ መዋደድ ፡ ነው ፡ ባልንጀ
ራህን ፡ እንደ ፡ ራስህ ፡ እየወደድህ ።
፳፫ ክፉ ፡ ነገር ፡ ባደረገብህ ፡ ሰውም ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡
ሳታደርግ ፡ መከራውን ፡ ለታገሡ ፡ ሰዎች ፡ ወደ ፡
ተሰጠ ፡ ወደ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ትገባ ፡
ዘንድ ፡ የከበረች ፡ መንግሥተ ፡ ሰማይን ፡ በዕ
ውቀትና ፡ በትዕግሥት ፡ ከከበሩ ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡
በትንሣኤም ፡ ጊዜ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማይን ፡
ተስፋ ፡ በማድረግ ፡ ዋጋህን ፡ ይሰጥህ ፡ ዘንድ ፡
በሚገባ ፡ መዋደድ ፡ ነው ።
፳፬ ይኽንን ፡ የሚናገሩ ፡ የሚያስቡን ፡ ሰዎች ፡ በት
ንሣኤም ፡ ጊዜ ፡ እንዳይድኑ ፡ ዲያብሎስ ፡ ተስፋ ፡
ያስቈርጣቸዋልና ፡ ከሞትን ፡ በኋላ ፡ እንነሣም ፡
አትበሉ ፡ ምጽአት ፡ በደረሰችባቸው ፡ ጊዜ ፡
ፍዳ ፡ እንዳለባቸው ፡ ያውቃሉ ፡ ኃጢአታቸ
ውን ፡ ያስባባቸው ፡ ዘንድ ፡ ባለማወቅ ፡ ኃጢ
አት ፡ የሠሩ ፡ ሰዎች ፡ በትንሣኤ ፡ ጊዜ ፡ ፈጽ
መው ፡ ያዝናሉ ፡ በዚያች ፡ ቀን ፡ እንዲነሡ ፡
አላመኑበትምና ።
ስለዚህ ፡ ነገር ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ እንደ ፡ ሠሩት ፡ ፳፭
ሥራቸው ፡ ክፋት ፡ መጠን ፡ ይወቀሳሉ ፡ በሥጋ ፡
አንድነት ፡ የሚነሡበት ፡ የካዱት ፡ ትንሣኤንም ፡
ያይዋቃል ።
በጎ ፡ ሥራን ፡ ስላልሠሩ ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ ያለቅሳሉ ፡ ፳፮
በገሃነም ፡ የሚያለቅሱ ፡ እንዳይሆኑ ፡ ቢቻላ
ቸው ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ቢያለቅሱ ፡ በተሻላቸው ፡
ነበር ።
በዚህ ፡ ዓለም ፡ በፈቃዳችን ፡ ካላለቀስን ፡ በገሃ ፳፯
ነም ፡ አጋንንት ፡ ያለፈቃዳችን ፡ ያስለቅሱናል ፡
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ንስሐ ፡ ካልገባን ፡ በገሃነም ፡ የማ
ይረባ ፡ የማይጠቅም ፡ ጩኸትን ፡ ልቅሶን ፡ እና
ዘጋጃለን ።
ከሞት ፡ ወደ ፡ ሕይወት ፡ ትሸገሩ ፡ ዘንድ ፡ ከም ፳፰
ታልፍ ፡ ከዚህች ፡ ዓለምም ፡ ወደ ፡ መንግሥተ ፡
ሰማይ ፡ ትሄዱ ፡ ዘንድ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ካለ ፡
ብርሃን ፡ የሚበልጥ ፡ የመንግሥተ ፡ ሰማይን ፡
ብርሃንንም ፡ ታዩ ፡ ዘንድ ፡ በጎ ፡ ሥራን ፡ አዘጋጁ ።
የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ መነሣትን ፡ ከሚያምኑ ፡ ሰዎች ፡ ፳፱
ጋራ ፡ ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዘላለሙ ፡ ድረስ ፡
በማይፈጸም ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ በመንግሥተ ፡
ሰማይ ፡ ያለ ፡ ልክ ፡ ደስ ፡ ይልህ ፡ ዘንድ ፡ በዚህ ፡
ዓለም ፡ ያለች ፡ ተድላ ፡ ደስታን ፡ እምቢ ፡ በላት ።

እግዚአብሔር ፡ ለዘላለሙ ፡ ክብር ፡ ምስጋና ፡
ይግባውና ፡ የመቃብያንን ፡ ነገር ፡ የሚናገር ፡
ሦስተኛው ፡ መጽሐፍ ፡ ተፈጸመ ።

# መጽሐፈ ፡ ሲራክ ።

ኢያሱ ፡ ሲራክ ፡ የተናገረው ፡ ነገር ፡ ይህ ፡
ነው ፤ ኢያሱ ፡ ማለት ፡ መድኃኒት ፡ ማለት ፡
ነው ፤ ሲራክ ፡ መለት ፡ ጸሐፊ ፡ ማለት ፡ ነው ፤
የኢየሩሳሌሙ ፡ ሰው ፡ የአልዓዛር ፡ ልጅ ፡ እኔ ፡
ኢያሱ ፡ ሲራክ ፡ ኢታምልክን ፡ ዘጠኙን ፡ ሕግ
ጋት ፡ በዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ ጻፍኩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ የጥበብ ፡ ሁሉ ፡ መገኛዋ ፡ ከእግዚአብሔር ፡
ዘንድ ፡ ነው ፡ ዓለም ፡ ሳይፈጠር ፡ ጥበብ ፡ ከርሱ ፡
ጋራ ፡ ነበረች ።
፪፤ የባሕር ፡ አሸዋን ፡ የዝናም ፡ ጠብታን ፡ የዘመ
ንን ፡ ቍጥር ፡ ማን ፡ ቈጠረ ።
፫፤ የሰማይን ፡ ምጥቀት ፡ የምድርን ፡ ስፋት ፡ የባሕ
ርን ፡ ጥልቀት ፡ ጥበብንም ፡ ማን ፡ መርምሮ ፡
አወቃቸው ።
፬፤ ጥበብ ፡ ከሁሉ ፡ አስቀድሞ ፡ ተፈጠረች ።
፭፤ የጥበብ ፡ መታሰቢ ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ ነው ።
፮፤ የጥበብ ፡ ምሥጢሯ ፡ ለማን ፡ ተገለጠ ።
፯፤ ምክሯንስ ፡ ማን ፡ አወቀ ።
፰፤ ጥበብ ፡ አንድ ፡ ነው ፡ በማያውቁት ፡ ሰዎች ፡
ዘንድ ፡ ፈጽሞ ፡ የሚያስፈሩ ፡ ነው ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ በዙፋኑ ፡ ላይ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ።
፱፤ እርሱ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጥበብን ፡ ሠራት ፡ አስ
ተማራት ፡ ሰፈራትም ።
፲፤ እንደ ፡ ስጦታው ፡ ሰው ፡ በሥጋዊ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡
አሳደራት ፡ ለሚወዷት ፡ ሰዎችም ፡ ሁሉ ፡ ሰጣ
ቸው ።
፲፩፤ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ ክብር ፡ ነው ፡ የሚ
ያስመካ ፡ ተድላ ፡ ደስታም ፡ ነው ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡
ያለው ፡ ዘውድም ፡ ነው ።
፲፪፤ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ የልብ ፡ ተድላ ፡
ደስታ ፡ ነው ፡ ተድላ ፡ ደስታን ፡ ይሰጣል ፡ ደስም ፡
ያሰኛል ፡ በሕይወት ፡ የሚኖሩበትንም ፡ ዘመን ፡
ያበዛል ።
፲፫፤ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈራ ፡ ሰው ፡ ፍጻሜው ፡
ያምራል ፡ በሚሞትበትም ፡ ቀን ፡ ይከብራል ።
፲፬፤ የጥበብ ፡ መጀመሪያ ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍ
ራት ፡ ነው ፡ ከናታቸው ፡ ማኅፀን ፡ ከተወለዱ ፡
በኋላ ፡ ለምዕመናን ፡ ታሠራለች ።
፲፭፤ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ ለሰው ፡ ተፈጠረች ፡ ከልጆቻ
ቸው ፡ ጋራ ፡ ጸንታ ፡ ልትኖር ፡ ታመነች ።
፲፮፤ ጥበብን ፡ መጥገብ ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡
ነው ፡ ምሥጢሩን ፡ ትገልጥላቸዋለች ።
፲፯፤ በመምህራን ፡ ጉባኤ ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ መል
ቷል ፡ በበታዋም ፡ ትምህርት ፡ አለ ።
፲፰፤ የጥበብ ፡ ዘውዷ ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡
ነው ፡ ፍቅር ፡ አንድነትን ፡ ያመጣታል ፡ ፈጽሞ ፡
ያድናል ።
፲፱፤ ጥበብን ፡ ፈጣሪዋ ፡ ሠራት ፡ ሰፈራትም ፡ ለሰ
ውም ፡ ገለጣት ፡ የምክርንና ፡ የውቀትን ፡ የጥ
በብንም ፡ ምሥጢር ፡ ገለጠ ፤ የሚያጸኗትንም ፡
ሰዎች ፡ አገነናቸው ፡ አከበራቸው ።
፳፤ የጥበብ ፡ መጀመሪያ ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍ
ራት ፡ ነው ፡ ሥራቷም ፡ በሕይወት ፡ የሚኖሩ
በትን ፡ ዘመን ፡ ያበዛል ።
፳፩፤ በተቈጣ ፡ ጊዜ ፡ መከራ ፡ ይመጣበታልና ፡ ቍጡ ፡
ዓመፀኛ ፡ ሰው ፡ አይጸድቅም ።
፳፪፤ ጊዜዋን ፡ እስክታሳልፍ ፡ ድረስ ፡ ቍጣን ፡ ታግ
ሣት ፡ ኋላ ፡ ደስ ፡ ታሰኝሃለች ።
፳፫፤ ጊዜውን ፡ እስክታገኝ ፡ ድረስ ፡ ነገርህን ፡ ሠውር ፡
ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ጥበብህን ፡ ይናገራሉ ።
፳፬፤ በመምራን ፡ ጉባኤ ፡ መስለው ፡ የሚያስተም
ሩት ፡ ትምህርት ፡ አለ ። ኃጢአተኛ ፡ ሰው ፡
እግዚአብሔርን ፡ የሚፈራ ፡ ሰውን ፡ ይጸየፈ
ዋል ።

ጥበብን ፡ ከወደድሃት ፡ ትእዛዙን ፡ ጠብቅ ፡ እግ ፳፭፤
ዚአብሔርም ፡ ጥበብን ፡ ይሰጥሃል ።
ጥበብ ፡ ይሉሃል ፡ እውቀት ፡ ይሉሃል ፡ እግዚአ ፳፮፤
ብሔርን ፡ መፍራት ፡ ነው ፡ ፈቃዱም ፡ ምግባ
ርና ፡ ሃይማኖት ፡ ነው ።
እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ አትዘንጋ ። ፳፯፤
እየተጠራጠርህ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ሁለት ፡ ፳፰፤
ልብ ፡ ሆነህ ፡ አታገልግለው ።
በሰው ፡ አፍ ፡ አትነስ ፡ ከንፈሮችህንም ፡ ክፉ ፡ ፳፱፤
ነገር ፡ ከመናገር ፡ ጠብቅ ።
እንዳትጐሰቍል ፡ ሰውነትህም ፡ በመከራ ፡ እን ፴፤
ዳትወድቅ ፡ ራስህን ፡ አታኰራ ። እግዚአብሔ
ርም ፡ ሠውረህ ፡ የሠራኸው ፡ ኃጢአትህን ፡
ይገልጥብሃል ። እግዚአብሔርን ፡ በመፍራ
ራት ፡ አልመጣህምና ፡ በብዙ ፡ ሰዎች ፡ መካከል ፡
በመከራ ፡ ይጥልሃል ። በልብህም ፡ ክዳት ፡ አለ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

ልጅ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ትገዛ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ፩፤
ገዳም ፡ ብትሄድ ፡ ሰውነትህን ፡ ለመከራ ፡ አዘ
ጋጅ ።
ልብህን ፡ በምግባር ፡ አቅና ፡ መከራውንም ፡ ፪፤
ታገሥ ፡ አትጠራጠር ፡ በመከራውም ፡ ብትጨ
ነቅ ፡ አትጠራጠር ።
ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ተከተለው ፡ ኋላ ፡ ፫፤
በፍጻሜ ፡ ዘመንህም ፡ ክብርህ ፡ ትበዛ ፡ ዘንድ ፡
አትተወው ።
የደረሰብህን ፡ መከራ ፡ ሁሉ ፡ በትዕግሥት ፡ ተቀ ፬፤፭፤
በል ። ወርቅን ፡ በእሳት ፡ እንዲፈትኑት ፡ ጻድ
ቅንም ፡ ሰው ፡ ችግርን ፡ በሚያመጣ ፡ መከራ ፡
ይፈትኑታልና ፡ ገንዘብ ፡ በተቸገርክበት ፡ ወራት ፡
መከራውን ፡ ታገሥ ።
እግዚአብሔርን ፡ እመነው ፡ እንጂ ፡ ይረዳሃል ፡ ፮፤
ሥራህን ፡ አቅና ፡ በሱም ፡ እመን ።
እግዚአብሔርን ፡ የምትፈሩት ፡ ሰዎች ፡ ቸርነ ፯፤
ቱን ፡ ደጅ ፡ ጥኗት ፡ በመከራ ፡ እንዳትወድቁ ፡
ከሱ ፡ አትራቁ ።
እግዚአብሔርን ፡ የምትፈሩት ፡ ሰዎች ፡ እመኑት ፡ ፰፤
ዋጋችሁንም ፡ እንዳታጡ ፡ ሁኑ ።
እግዚአብሔርን ፡ የምትፈሩ ፡ ሰዎች ፡ በጎ ፡ ረድ ፱፤
ኤቱን ፡ ተስፋ ፡ አድርጓት ፡ ዘለዓለም ፡ ጸንቶ ፡
የሚኖር ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ቸርነቱን ፡ ተስፋ ፡
አድርጉ ።
በዘመን ፡ የቀደሙ ፡ ሰዎችን ፡ አስተውሉ ፡ በእ ፲፤
ግዚአብሔር ፡ አምኖ ፡ ያፈረ ፡ ማነው ። እወቁ ፡
እሱን ፡ በመፍራት ፡ መከራውን ፡ የታገሠ ፡
በመከራ ፡ እንደ ፡ ጣለው ፡ የቀረ ፡ ማነው ። ለም
ኖትስ ፡ ቸል ፡ ያለው ፡ ማናው ።
እግዚአብሔር ፡ ይቅር ፡ ባይ ፡ ነውና ፡ ርኅሩኅ ፡ ፲፩፤
ነውና ፡ ኃጢአትን ፡ ይቅር ፡ ይላል ፡ ከመከራም ፡
ቀን ፡ ያድናል ።
ለሚጠራጠር ፡ ልቡና ፡ ወዮለት ፡ ለክፉዎች ፡ ፲፪፤
ሰዎች ፡ ወዮላቸው ፡ ሥራው ፡ ሁለት ፡ ለሆነ ፡
ኃጢአቱንም ፡ አብዝቶ ፡ ለሚሠራ ፡ ለኃጢአ
ተኛ ፡ ሰው ፡ ወዮለት ።
ለሚጠራጠር ፡ ሰው ፡ ወዮለት ፡ አላመነምና ፡ ፲፫፤
ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ከመከራው ፡ አያመልጥም ።
ዋጋቸውን ፡ ላጡ ፡ ሰዎች ፡ ወዮላቸው ፡ እግዚ ፲፬፤
አብሔር ፡ በመዓት ፡ በተመላበቸው ፡ ጊዜ ፡ ምን ፡
ያደርጉ ፡ ይሆን ።
እግዚአብሔርን ፡ የሚፈሩ ፡ ሰዎች ፡ ቃሉን ፡ አይ ፲፭፤
ረሱም ፡ የሚወዱትም ፡ ሰዎች ፡ አምልኮቱን ፡
ዘጠኙን ፡ ሕግጋት ፡ ይጠብቃሉ ።
እግዚአብሔርን ፡ የሚፈሩ ፡ ሰዎች ፡ ፈቃዱን ፡ ፲፮፤
ይፈጽማሉ ፡ የሚወዱትም ፡ ሰዎች ፡ ሕጉን ፡

፱፤ እርሱ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጥበብን ፡ ሠራት ፡ አስ
ተማራት ፡ ሰፈራትም ።
፲፤ እንደ ፡ ስጦታው ፡ ሰው ፡ በሥጋዊ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡
አሳደራት ፡ ለሚወዷት ፡ ሰዎችም ፡ ሁሉ ፡ ሰጣ
ቸው ።
፲፩፤ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ ክብር ፡ ነው ፡ የሚ
ያስመክ ፡ ተድላ ፡ ደስታም ፡ ነው ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡
ያለው ፡ ዘውድም ፡ ነው ።
፲፪፤ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ የልብ ፡ ተድላ ፡
ደስታ ፡ ነው ፡ ተድላ ፡ ደስታን ፡ ይሰጣል ፡ ደስም ፡
ያሰኛል ፡ በሕይወት ፡ የሚኖሩበትንም ፡ ዘመን ፡
ያበዛል ።
፲፫፤ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈራ ፡ ሰው ፡ ፍጻሜው ፡
ያምራል ፡ በሚሞትበትም ፡ ቀን ፡ ይከብራል ።
፲፬፤ የጥበብ ፡ መጀመሪያ ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍ
ራት ፡ ነው ፡ ከናታቸው ፡ ማኅፀን ፡ ከተወለዱ ፡
በኋላ ፡ ለምዕመናን ፡ ታሥራለች ።
፲፭፤ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ ለሰው ፡ ተፈጠረች ፡ ከልጆቻ
ቸው ፡ ጋራ ፡ ጸንታ ፡ ልትኖር ፡ ታምናች ።
፲፮፤ ጥበብን ፡ መጥገብ ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡
ነው ፡ ምሥጢሩን ፡ ትገልጥላቸዋለች ።
፲፯፤ በመምህራን ፡ ጉባኤ ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ መል
ቷል ፡ በበታዋም ፡ ትምህርት ፡ አለ ።
፲፰፤ የጥበብ ፡ ዘውዱ ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡
ነው ፡ ፍቅር ፡ አንድነትን ፡ ያመጣታል ፡ ፈጽሞ ፡
ያድናል ።
፲፱፤ ጥበብን ፡ ፈጣሪዋ ፡ ሠራት ፡ ሰፈራትም ፡ ለሰ
ውም ፡ ገለጣት ፡ የምክርንና ፡ የውቀትን ፡ የጥ
በብንም ፡ ምሥጢር ፡ ገለጠ ፡ የሚያጸኗትንም ፡
ሰዎች ፡ አገነናቸው ፡ አከበራቸው ።
፳፤ የጥበብ ፡ መጀመሪያ ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍ
ራት ፡ ነው ፡ ሥራቷም ፡ በሕይወት ፡ የሚኖሩ
በትን ፡ ዘመን ፡ ያበዛል ።
፳፩፤ በተቈጣ ፡ ጊዜ ፡ መከራ ፡ ይመጣበታልና ፡ ቍጡ ፡
ዓመፀኛ ፡ ሰው ፡ አይጸድቅም ።
፳፪፤ ጊዜዋን ፡ እስክታሳልፍ ፡ ድረስ ፡ ቍጣን ፡ ታገ
ሣት ፡ ኋላ ፡ ደስ ፡ ታሰኝሃለች ።
፳፫፤ ጊዜውን ፡ እስክታገኝ ፡ ድረስ ፡ ነገርህን ፡ ሠውር ፡
ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ጥበብህን ፡ ይናገራሉ ።
፳፬፤ በመምራን ፡ ጉባኤ ፡ መስለው ፡ የሚያስተም
ሩት ፡ ትምህርት ፡ አለ ። ኃጢአተኛ ፡ ሰው ፡
እግዚአብሔርን ፡ የሚፈራ ፡ ሰውን ፡ ይጸየፈ
ዋል ።
፳፭፤ ጥበብን ፡ ከወደድሃት ፡ ትእዛዙን ፡ ጠብቅ ፡ እግ
ዚአብሔርም ፡ ጥበብን ፡ ይሰጥሃል ።
፳፮፤ ጥበብ ፡ ይሉሃል ፡ እውቀት ፡ ይሉሃል ፡ እግዚአ
ብሔርን ፡ መፍራት ፡ ነው ፡ ፈቃዱም ፡ ምግበ
ርና ፡ ሃይማኖት ፡ ነው ።
፳፯፤ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ አትዘንጋ ።
፳፰፤ እየተጠራጠርህ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ሁለት ፡
ልብ ፡ ሆነህ ፡ አታገልግለው ።
፳፱፤ በሰው ፡ አፍ ፡ አትነስ ፡ ከንፈሮችህንም ፡ ክፉ ፡
ነገር ፡ ከመናገር ፡ ጠብቅ ።
፴፤ እንዳትጐሰቍል ፡ ሰውነትህም ፡ በመከራ ፡ እን
ዳትወድቅ ፡ ራስህን ፡ አታኩራ ። እግዚአብሔ
ርም ፡ ሠውረህ ፡ የሠራኸው ፡ ኃጢአትህን ፡
ይገልጥብሃል ። እግዚአብሔርን ፡ በመፍራ
ራት ፡ አልመጣህምና ፡ በብዙ ፡ ሰዎች ፡ መካከል ፡
በመከራ ፡ ይጥልሃል ። በልብህም ፡ ክዳት ፡ አለ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

ልጄ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ትገዛ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፩፤
ገዳም ፡ ብትሄድ ፡ ሰውነትህን ፡ ለመከራ ፡ አዘ
ጋጅ ።
ልብህን ፡ በምግባር ፡ አቅና ፡ መከራውንም ፡ ፪፤
ታገሥ ፡ አትጠራጠር ፡ በመከራውም ፡ ብትጨ
ነቅ ፡ አትጠራጠር ።
ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ተከተለው ፡ ኋላ ፡ ፫፤
በፍጻሜ ፡ ዘመንህም ፡ ክብርህ ፡ ትበዛ ፡ ዘንድ ፡
አትተወው ።
የደረሰብህን ፡ መከራ ፡ ሁሉ ፡ በትዕግሥት ፡ ተቀ ፬፤፭፤
በል ። ወርቅን ፡ በእሳት ፡ እንዲፈትኑት ፡ ጻድ
ቅንም ፡ ሰው ፡ ችግርን ፡ በሚያመጣ ፡ መከራ ፡
ይፈትኑታልና ፡ ገንዘብ ፡ በተቸገርክበት ፡ ወራት ፡
መከራውን ፡ ታገሥ ።
እግዚአብሔርን ፡ እመነው ፡ እንጂ ፡ ይረዳሃል ፡ ፮፤
ሥራህን ፡ አቅና ፡ በሱም ፡ እመን ።
እግዚአብሔርን ፡ የምትፈሩት ፡ ሰዎች ፡ ቸርነ ፯፤
ቱን ፡ ደጅ ፡ ጥኗት ፡ በመከራ ፡ እንዳትወድቁ ፡
ከሱ ፡ አትራቁ ።
እግዚአብሔርን ፡ የምትፈሩት ፡ ሰዎች ፡ እመኑት ፡ ፰፤
ዋጋችሁንም ፡ እንዳታጡ ፡ ሁኑ ።
እግዚአብሔርን ፡ የምትፈሩ ፡ ሰዎች ፡ በጎ ፡ ረድ ፱፤
ኤቱን ፡ ተስፋ ፡ አድርጓት ፡ ዘለዓለም ፡ ጸንቶ ፡
የሚኖር ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ቸርነቱን ፡ ተስፋ ፡
አድርጉ ።
በዘመን ፡ የቀደሙ ፡ ሰዎችን ፡ አስተውሉ ፡ በእ ፲፤
ግዚአብሔር ፡ አምኖ ፡ ያፈረ ፡ ማነው ። እወቁ ፡
እሱን ፡ በመፍራት ፡ መከራውን ፡ የታገሠ ፡
በመከራ ፡ እንደ ፡ ጣለው ፡ የቀረ ፡ ማነው ። ለም
ኖትስ ፡ ቸል ፡ ያለው ፡ ማናው ።
እግዚአብሔር ፡ ይቅር ፡ ባይ ፡ ነውና ፡ ርኅሩኅ ፡ ፲፩፤
ነውና ፡ ኃጢአትን ፡ ይቅር ፡ ይላል ፡ ከመከራም ፡
ቀን ፡ ያድናል ።
ለሚጠራጠር ፡ ልቡና ፡ ወዮለት ፡ ለክፉዎች ፡ ፲፪፤
ሰዎች ፡ ወዮላቸው ፡ ሥራው ፡ ሁለት ፡ ለሆነ ፡
ኃጢአቱንም ፡ አብዝቶ ፡ ለሚሠራ ፡ ለኃጢአ
ተኛ ፡ ሰው ፡ ወዮለት ።
ለሚጠራጠር ፡ ሰው ፡ ወዮለት ፡ አላመነምና ፡ ፲፫፤
ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ከመከራው ፡ አያመልጥም ።
ዋጋቸውን ፡ ላጡ ፡ ሰዎች ፡ ወዮላቸው ፡ እግዚ ፲፬፤
አብሔር ፡ በመዓቱ ፡ በተመላበቸው ፡ ጊዜ ፡ ምን ፡
ያደርጉ ፡ ይሆን ።
እግዚአብሔርን ፡ የሚፈሩ ፡ ሰዎች ፡ ቃሉን ፡ አይ ፲፭፤
ረሱም ፡ የሚወዱትም ፡ ሰዎች ፡ አምልክቱን ፡
ዘጠኙን ፡ ሕግጋት ፡ ይጠብቃሉ ።
እግዚአብሔርን ፡ የሚፈሩ ፡ ሰዎች ፡ ፈቃዱን ፡ ፲፮፤
ይፈጽማሉ ፡ የሚወዱትም ፡ ሰዎች ፡ ሕጉን ፡

ይጠብቃሉ ።
፲፯፤ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈሩ ፡ ሰዎች ፡ ልቡናቸ
ውን ፡ ለመከራ ፡ ያዘጋጃሉ ። ሰውነታቸውንም ፡
መከራውን ፡ ያስቧታል ፡ ቸርነቱ ፡ እንደ ፡ ገናን
ነቱ ፡ ብዛት ፡ መጠን ፡ ነውና ።
፲፰፤ በሰው ፡ እጅ ፡ ከመውደቅ ፡ በእግዚአብሔር ፡
እጅ ፡ መውደቅ ፡ ይሻላልና ፡ ብለው ፡ ሰውነታ
ቸውን ፡ በፊቱ ፡ መከራውን ፡ ያስችሏታል ።

ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩፤ ልጆቼ ፡ እኔን ፡ አባታችሁን ፡ ስሙኝ ፡ አባ
ትን ፡ በልጆች ፡ ላይ ፡ አክብሯልና ።
፪፤ የእናትንም ፡ አገዛዝ ፡ በልጆቿ ፡ ላይ ፡ አክብሯ
ልና ።
፫፤ አባቱን ፡ የሚያከብር ፡ ልጅ ፡ ኃጢአቱ ፡ ይሠረ
ይለታል ።
፬፤ እናቱንም ፡ የሚያከብራት ፡ ልጅ ፡ ድልብ ፡ እንደ
ሚያደልብ ፡ ሰው ፡ ነው ።
፭፤ አባቱን ፡ የሚያከብር ፡ ልጅ ፡ በልጁ ፡ ደስ ፡ ይለ
ዋል ፡ በለመነበትም ፡ ቀን ፡ ጸሎቱን ፡ ፈጣሪው ፡
ይሰማዋል ።
፮፤ አባቱን ፡ የሚያከብር ፡ ልጅ ፡ ዘመኑ ፡ ይበዛ
ለታል ።
፯፤ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ የሚሰማ ፡ ልጅ ፡ እና
ቱን ፡ ያሳርፋታል ።
፰፤ ባሮቹ ፡ ለሱ ፡ እንዲገዙለት ፡ እሱም ፡ ለወለ
ደው ፡ ላባቱ ፡ ይገዛል ።
፱፤ ምርቃቱ ፡ ትደርስልህ ፡ ዘንድ ፡ ቢጠራህ ፡ አቤት ፡
ቢልክህ ፡ ወዴት ፡ ብለህ ፡ አባትህን ፡ አክብረው ።
፲፤ ያባት ፡ ምርቃት ፡ የልጅን ፡ ቤት ፡ ያጸናልና ፡
የናት ፡ እርግማን ፡ ግን ፡ ስር ፡ መሠረት ፡ ይነቅ
ላል ።
፲፩፤ ልጅ ፡ ባባቱ ፡ ክብር ፡ የሚከብር ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡
እናቱንም ፡ መናቅ ፡ ማቃለል ፡ ሰውን ፡ የሚያ
ዋርደው ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ አባትህን ፡ መናቅ ፡ ማቃ
ለል ፡ መመኪያ ፡ አይሆንህምና ፡ አባትህን ፡ በመ
ናቅ ፡ አትመካ ።
፲፪፤ ልጄ ፡ በርጅናው ፡ ጊዜ ፡ አባትህን ፡ እርዳው ፡
በኑልበትም ፡ ሳለ ፡ አታሳዝነው ።
፲፫፤ ቢያረጅ ፡ አእምሮውንም ፡ ቢያጣ ፡ ፈቃዱን ፡
ለመፈጸም ፡ እሺ ፡ በለው ፡ ግን ፡ እንደሚቻ
ልህ ፡ አክብረው ፡ ዋጋ ፡ በመቀበል ፡ ጊዜ ፡ አባ
ትህን ፡ መርዳትህ ፡ አይዘነጋብህምና ። በረጅ ፡
ጊዜ ፡ አባትህን ፡ አትናቀው ።
፲፬፤ ስለ ፡ ኃጢአትም ፡ ፈንታ ፡ ጽድቅ ፡ ትሠራልሃ
ለች ።
፲፭፤ በመከራህም ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ ያስብል
ሃል ፡ በረድን ፡ ፀሐይ ፡ እንዲያቀልጠው ፡ ኃጢ
አቶችህ ፡ እንደዚሁ ፡ ይቀልጣሉ ። (ይሠረዩ
ልሃል ፡)
፲፮፤ አባቱን ፡ የሚጠላ ፡ ሰው ፡ የተነቀፈ ፡ ነው ፡ እና
ቱን ፡ የሚያሳዝናት ፡ ሰው ፡ በእግዚአብሔር ፡
ዘንድ ፡ የተረገመ ፡ ነው ።

ልጄ ፡ በሃይማኖትህ ፡ ላይ ፡ ሥራህ ፡ ይገለጥ ፡ ፲፯፤
እውነተኞች ፡ ሰዎችም ፡ ይወዱሃል ። (ደጎች ፡
ሰዎች ፡)
እንደገናንነትህ ፡ ብዛት ፡ መጠን ፡ እንደዚሁ ፡ ፲፰፤
ራስህን ፡ አዋርድ ። በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡
ዋጋህን ፡ ታገኛለህ ።
የእግዚአብሔር ፡ ሥራው ፡ ልዑል ፡ ነውና ፡ ፲፱፤
በተዋረዱ ፡ በጸኑ ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ ይመሰገናል ።
ከባለጸጋ ፡ ጋራ ፡ አትከራከር ፡ የታዘዝከውን ፡ ፳፤
አስብ ፡ እንጂ ፡ የማትችለውን ፡ ነገር ፡ አትመር
ምር ።
ወደ ፡ እልፍኙ ፡ ግን ፡ አያገባህም ። ፳፩፤
ሥላሴ ፡ ከሰው ፡ ይልቅ ፡ የገለጡልህ ፡ ምሥ ፳፪፤
ጢር ፡ የለምና ፡ ከግብር ፡ ገብተህ ፡ ብሕርየ ፡
ሥላሴን ፡ አትመርምር ።
ብዙ ፡ ሰዎችን ፡ መቃለያቸው ፡ አሳታቸው ። ፳፫፤
ብዙ ፡ ሰዎችን ፡ የልቡናቸው ፡ ትዕቢት ፡ በመ
ከራ ፡ ጣላቸው ።
ክህደትን ፡ የሚወዳት ፡ ሰው ፡ በሷ ፡ ይሞታል ፡ ፳፬፤
ክፉ ፡ ልቡናም ፡ በፍጻሜ ፡ ዘመኑ ፡ ለሥራ ፡ ይያ
ዛል ።
ክፉ ፡ ልቡና ፡ በመከራ ፡ ይገረፋል ፡ ኃጢአተኛ ፡ ፳፭፤
ሰውም ፡ በኃጢአቶቹ ፡ ላይ ፡ ኃጢአትን ፡ ይጨ
ምራል ።
ክፉ ፡ ክህደት ፡ ጸንቶባቸዋልና ፡ ለትዕቢተኞች ፡ ፳፮፤
ሰዎች ፡ ክህደት ፡ መመለስ ፡ የላትም ።
የብልህ ፡ ሰው ፡ ልቡና ፡ ምሳሌን ፡ ይተረጉማል ፡ ፳፯፤
ያጥቂ ፡ ሰው ፡ ገሮም ፡ ጥበብ ፡ መስማትን ፡
ትወዳለች ።
የምትነድ ፡ እሳትን ፡ ውኃ ፡ ያጠፋታል ። እንደ ፳፰፤
ዚህም ፡ ሁሉ ፡ ምጽዋት ፡ ኃጢአትን ፡ ታስተ
ሠርያለች ።
ምጽዋትን ፡ ለሚሰጥ ፡ ሰው ፡ በፍጻሜ ፡ ዘመኑ ፡ ፳፱፤
እግዚአብሔር ፡ ዋጋውን ፡ ያስብለታል ፡ በመከ
ራም ፡ በተሰነከከለ ፡ ጊዜ ፡ የሚድንበት ፡ ረድ
ኤት ፡ ይገኛል ።

ምዕራፍ ፡ ፬ ።

ልጄ ፡ ድኃውን ፡ ምጽዋቱን ፡ አትከልክለው ፡ ፩፤
ከሚለምንህ ፡ ከድኃውም ፡ ዓይኖችህን ፡ አት
መልስ ።
የተራበች ፡ ሰውነትን ፡ አታሳዝን ፡ ያዘነ ፡ ሰው ፪፤
ንም ፡ አታበሳጭ ።
ያዘነ ፡ ልቡናን ፡ አታስደንግጥ ፡ የሚለምንህን ፡ ፫፤
ሰው ፡ አልፈኸው ፡ አትሒድ ።
የሚገዛልህ ፡ ቤተ ፡ ሰብህን ፡ አትቈጣ ፡ ከድ ፬፤
ኃም ፡ ፊትህን ፡ አትመልስ ።
ከሚለምንህ ፡ ሰው ፡ ፊትህን ፡ አትመልስ ፡ በል ፭፤
ቡናው ፡ አዝኖ ፡ ቢረግምህ ፡ ፈጣሪው ፡ ልመና
ውን ፡ ይሰማዋልና ።
ለሚረግምህ ፡ ሰው ፡ ገንዘብ ፡ ምክንያት ፡ አትስ ፮፤
ጠው ።
ቤብዙ ፡ ሰዎች ፡ ዘንድ ፡ እንድትወደድ ፡ ሁን ፡ ፯፤
ዳኞችን ፡ አገልግል ፡ ራስህንም ፡ አታኰራ ።

፰ ድኃውን ፡ በጆሮህ ፡ አድምጠው ፡ በየዋህነት ፡
በጎ ፡ ቃልንም ፡ መልስለት ።
፱ የተበደለውንም ፡ ሰው ፡ ከሚበድለው ፡ ሰው ፡
እጅ ፡ አድነው ፡ ለሱም ፡ መፍረድ ፡ ቸል ፡
አትበል ።
፲ እናት ፡ አባቱ ፡ ለሞተበትም ፡ ልጅ ፡ እንዳባቱ ፡
ሁነው ፡ ለናቱም ፡ እንደ ፡ ባሏ ፡ ቁምላት ፥ እንደ ፡
እግዚአብሔር ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ ጻድቃን ፡ ትሆ
ናለህ ፡ ከናትህ ፡ ይልቅ ፡ ይወድሃል ።
፲፩ ጥበብስ ፡ ልጆቿን ፡ አገነነቻቸው ፡ የሚፈልጓት
ንም ፡ ሰዎች ፡ ትቀበላቸዋለች ።
፲፪ እሷን ፡ የወደደ ፡ ሰው ፡ ሕይወቱን ፡ ወደደ ፡
ወደሷም ፡ የሚገሠግሥ ፡ ሰው ፡ ተድላ ፡ ደስ
ታን ፡ ይጸግባል ።
፲፫ የሚያጸናትም ፡ ሰው ፡ ክብርን ፡ ይወርሳል ፡
እሷም ፡ ከደረሰችበት ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡
ያከብራል ።
፲፬ እሷንም ፡ የሚያገለግሉ ፡ ሰዎች ፡ እግዚአብ
ሔርን ፡ አገለገሉት ፡ የሚወዷትንም ፡ ሰዎች ፡
እግዚአብሔር ፡ ይወዳቸዋል ።
፲፭ እሷን ፡ የሚሰማት ፡ ሰው ፡ አሕዛብን ፡ ይገዛል ፡
እሷንም ፡ የሚያደምጣት ፡ ሰው ፡ ከመከራው ፡
ተዘልሎ ፡ ይኖራል ።
፲፮ ከመንኻት ፡ ስትረዳህ ፡ ታገኛታለህ ፡ በዘመን
ህም ፡ ታገንሃለች ፡ ታከብርሃለች ።
፲፯ ጠላቱን ፡ ፈጽማ ፡ እያስፈራራችለት ፡ እያስደነ
ግጠችለት ፡ ለመከራ ፡ እየገረፈችለት ፡ ሰውነ
ቱን ፡ እስከታስገዛለት ፡ ድረስ ፡ እያስተማረችው ፡
በምክርም ፡ እየፈተነችው ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ ጸንታ ፡
ትኖር ፡ ዘንድ ፡ አስቀድማ ፡ ትስጠዋለች ።
፲፰ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ዳግመኛ ፡ በረድኤት ፡ ተቀብላ ፡
ደስ ፡ ታሰኘዋለች ፡ ምክሩንም ፡ ትገልጥለታ
ለች ።
፲፱ ከሷ ፡ ወጥቶ ፡ ቢስት ፡ ግን ፡ ትለየዋለች ። በሚ
ጥለው ፡ በጠላቱም ፡ እጅ ፡ ትጥለዋለች ።
፳ ክፉ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አውቀህ ፡ ጊዜውን ፡ ተጠ
በቅ ፡ ሰውን ፡ አፍሮ ፡ ኃጢአት ፡ የሚሠራ ፡
አለና ፡ ሰውነትህን ፡ ለመጕዳት ፡ ሰው ፡ አፍረህ ።
፳፩ ፍርድ ፡ አታድላ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አፍሮ ፡
ጽድቅ ፡ የሚሠራ ፡ ሰው ፡ አለና ፡ መወደድን ፡
ያገኛል ።
፳፪ ነገሩ ፡ ለሰውነትህ ፡ እየተረዳህ ፡ የሰው ፡ ፊት ፡
አይተህ ፡ ፍርድ ፡ አታድላ ፡ ሰውነትህን ፡ እንዳ
ታጠፋ ፡ ዘንድ ፡ አትፈር ።
፳፫ ከቃሉ ፡ የተነሣ ፡ ጥበቡ ፡ ይታወቃልና ፡ ትምህ
ርቱም ፡ ባንደበቱ ፡ ከመናገር ፡ የተነሣ ፡ ይታወ
ቃልና ፡ የሚናገርን ፡ ሰው ፡ ቆይ ፡ እኔ ፡ ልናገር ፡
ብለህ ፡ አትከልክለው ።
፳፬ ያልሆነ ፡ ሃይማኖት ፡ ይዘህ ፡ ስለ ፡ ሃይማኖት ፡
አትከራከር ። ስለ ፡ በደልኸውም ፡ በደል ፡
ንስሐ ፡ ገብተህ ፡ ተለማመጥ ።
፳፭ ኃጢአትህንም ፡ መናገር ፡ አትፈር ፡ እንደ ፡ ዓባይ ፡
ያለውን ፡ ውኃ ፡ በሐምሌ ፡ በነሐሴ ፡ እሻገራለሁ ፡
አትበል ።
፳፮ ለሰነፍ ፡ ሰው ፡ ራስህን ፡ አታዋርድ ፡ ለባለጸጋ ፡
አታድላ ።
ፈጣሪህ ፡ እግዚአብሔር ፡ ስላንተ ፡ ይከራከርል ፳፯
ሃልና ፡ እስክትሞት ፡ ድረስ ፡ በሃይማኖት ፡ አት
ከራከር ።
በፍህ ፡ አውታታ ፡ አትሁን ፡ ሥራህንም ፡ ቸል ፡ ፳፰
አትበል ።
በቤትህም ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ አትገረም ፡ በው ፳፱
ነት ፡ የሚገዛልህ ፡ ቤተ ፡ ሰብህንም ፡ አታስገዝን ።
በምትከፍልበት ፡ ጊዜ ፡ ቀኝ ፡ እጅህን ፡ ትሰበ ፴
ስብ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ መሰብሰብ ፡ እንዳትመለስ ፡
ለመበደር ፡ እጅህን ፡ አትዘርጋ ።

## ምዕራፍ ፡ ፭ ።

ገንዘብህን ፡ በከንቱ ፡ አትበትን ፡ ገንዘብ ፡ በቃኝ ፡ ፩
አትበል ።
የሰውነትህን ፡ ፈቃድ ፡ አትከተል ። ፪
እግዚአብሔር ፡ ተበቃሎ ፡ ያጠፋልና ፡ እኔ ፡ ኃይ ፫
ለኛ ፡ ነኝ ፡ ማን ፡ ይችለኛል ፡ አትበል ።
እግዚአብሔር ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ ይታገሣልና ፡ ፬
ኃጢአት ፡ ሠርቼ ፡ ፍዳ ፡ አልተቀበልሁም ፡ አት
በል ።
ስለ ፡ ኃጢአትህ ፡ ንስሐ ፡ መግባትን ፡ አትፍራ ። ፭
የእግዚአብሔር ፡ ቸርነቱ ፡ ብዙ ፡ ነው ፡ እያልክ ፡
በኃጢአት ፡ ላይ ፡ ኃጢአት ፡ አትሥራ ።
ቸርነትም ፡ መቅሠፍትም ፡ ከርሱ ፡ ዘንድ ፡ ይመ ፮
ጣልና ፡ መቅሠፍቱ ፡ በኃጢአተኛ ፡ ሰው ፡ ላይ ፡
ይመጣል ።
ለእግዚአብሔር ፡ መገዛትን ፡ ቸል ፡ አትበል ። ፯
ሞት ፡ ድንገት ፡ ትመጣለችና ፡ ከቀን ፡ ቀን ፡ አታ
ሳልፍ ፡ ፍዳህ ፡ ከመቅሠፍት ፡ ጋራ ፡ በመጣብህ ፡
ጊዜ ፡ በመከራ ፡ ትጨነቃለህ ።
በመከራህ ፡ ጊዜ ፡ አንተን ፡ ማዳን ፡ አይችል ፰
ምና ፡ ቀምተህ ፡ ላመጣኸው ፡ ገንዘብ ፡ አትሳሳ ።
ለሰው ፡ ሁሉ ፡ ምሥጢርህን ፡ አታውጣ ። የወ ፱
ደድኸውን ፡ ሁሉ ፡ አትከተል ፡ ላንዱ ፡ እው
ነት ፡ ላንዱ ፡ አሰት ፡ እንደሚናገር ፡ እንደ ፡ ኃጢ
አተኛ ፡ ሰው ፡ አትሁን ።
አንተስ ፡ በጥበብህ ፡ ጸንተህ ፡ ኑር ፡ ቃልህም ፡ ፲
አንድ ፡ ይሁን ።
ፈጥነህ ፡ ስማ ፡ ቃልን ፡ ለመመለስ ፡ ግን ፡ የታገ ፲፩
ሥህ ፡ ሁን ።
ጠላቱን ፡ እስክታስፈራለት ፡ ድረስ ፡ እስክታስ ፲፪
ገርምለት ፡ እስክታስደነግጥለት ፡ እስክትቀሥ
ፍለት ፡ እስክታስተምረው ፡ ድረስ ፡ ደርሳ ፡ ሰው
ነቱንም ፡ እስክታስገዛለት ፡ ድረስ ፡ ደርሳ ፡ በመ
ከራም ፡ እስክትፈትነው ፡ ድረስ ፡ ደርሳ ፡ ከሱ ፡
ጋራ ፡ ጸንታ ፡ ትኖር ፡ ዘንድ ፡ አስቀድማ ፡ ትሰ
ጠዋለች ፡ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ቢተዋት ፡ ትቀ
በለዋለች ፡ ምክሩንም ፡ ትገልጥለታለች ፡ ከሷ ፡
ወጥቶ ፡ ቢሄድ ፡ ግን ፡ ትለየዋለች ፡ በሚገና
ኘው ፡ በጠላቱም ፡ እጅ ፡ ትጥለዋለች ።
እምትነግረው ፡ እንዳለ ፡ ለባልንጀራህ ፡ ንገ ፲፫
ረው ፡ የምትነግረው ፡ ነገር ፡ ከሌለ ፡ ግን ፡ እጅ
ህን ፡ በፍህ ፡ ላይ ፡ አድርገህ ፡ ዝም ፡ በል ።
መከበርህና ፡ መዋረድህ ፡ ከቃልህ ፡ የተነሣ ፡ ፲፬

ነው ። የሰው ፡ መከራው ፡ በንደበቱ ፡ ከተናገ
ረው ፡ ነገር ፡ የተነሣ ፡ ነው ።
፲፭ አሚተኛ ፡ አትሁን ፡ በንደበትህ ፡ አውታታ ፡
አትሁን ፡ የሌባ ፡ እፍረቱ ፡ ጥቂት ፡ ነው ። ልቡ
ናው ፡ ሁለት ፡ ነገር ፡ የሚያስብ ፡ ሰው ፡ ግን ፡
መከራው ፡ጽኑ ፡ ነው ። በታላቁም ፡ በታና
ሹም ፡ ሰው ፡ ዘንድ ፡ ቸር ፡ ሆነህ ፡ ተገለጥ ።

ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ የከፉ ፡ ስም ፡ ፍጻሜው ፡ ስድብና ፡ ውርደት ፡
ነውና ፡ ጠላት ፡ ከምትሆን ፡ ወዳጅ ፡ ሁን ፡ አን
ደበቱ ፡ ሁለት ፡ የሆነ ፡ ኃጢአተኛ ፡ ሰውም ፡
እንዲሁ ፡ ነው ። ( ላንዱ ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ ላንዱ ፡
አንድ ፡ ነገር ፡ የሚናገር ፡ )
፪ አንበሳ ፡ ላምን ፡ እንዲነጣጠቅ ፡ አሕዛብ ፡ ሰው
ነትህን ፡ በሞት ፡ እንዳይነጣጠቋት ፡ ከልቡናህ ፡
ባነቃኸው ፡ ምክር ፡ ራስህን ፡ አታሠራ ።
፫ አረማዊ ፡ ቅጠልህን ፡ ይበላብሃል ፡ ( ግምጃህን ፡
ያጠፋብሃል ፡ ) ፍሬህንም ፡ ታጣለህ ፡ ( ወርቅ
ህን ፡ ) እንደ ፡ ደረቅ ፡ እንጨትም ፡ ይጥልሃል ።
፬ ክፉ ፡ ሰውነት ፡ ገንዘብ ፡ ያደረጋትን ፡ ሰው ፡
ታጠፋዋለች ፡ ጠላቱንም ፡ በሱ ፡ የጨከነ ፡ ታደ
ርገዋለች ።
፭ ልዝብ ፡ አንደበት ፡ ወንድሚ ፡ ወንድሚ ፡ ማለ
ትን ፡ ያበዛል ፡ ልዝብ ፡ አፍም ፡ ወዳጅን ፡ ያበ
ዛል ።
፮ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ወዳጆችን ፡ ይሁኑህ ፡ ነገር ፡ ግን ፡
ከብዙዎቹ ፡ አንዱ ፡ ምክርህን ፡ ከምትናገር ፡
ከልቡናህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ይሁን ።
፯ ወዳጅ ፡ ባበጀህ ፡ ጊዜ ፡ በችጋርህ ፡ ወራት ፡
አብጅ ።
፰ ነገር ፡ ግን ፡ ወረተኛ ፡ ለጥቂት ፡ ቀን ፡ የሚሆን ፡
ወዳጅ ፡ አለና ፡ በመከራህም ፡ ጊዜ ፡ ካንተ ፡
ጋራ ፡ መከራህን ፡ አይታገሥምና ፡ ፈጽመህ ፡
አትመነው ።
፱ ጠላት ፡ የሚሆንህ ፡ የሚለገድህ ፡ ይሰድብሃል ።
ሠውረህ ፡ የሠራኸውን ፡ ኃጢአትህንም ፡ የሚ
ገልጥብህ ፡ ወዳጅ ፡ አለ ።
፲ ስለ ፡ ማዕድህም ፡ የሚወድህ ፡ ወዳጅ ፡ አለ ፡
እሱም ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ አይኖርም ፡ ከተቸገር
ህም ፡ በኋላ ፡ ይለይሃል ።
፲፩ በተሾምህ ፡ ጊዜ ፡ እንዳንተ ፡ ይሆናል ፡ ቤተ ፡
ሰብህንም ፡ ይገዛል ።
፲፪ ብትቸገር ፡ ግን ፡ እሱ ፡ ባለጋራህ ፡ ይሆናል ፡
እንዳታየውም ፡ ይሠወርሃል ።
፲፫ ከጠላቶችህ ፡ ራቅ ፡ ወዳጅ ፡ መስለው ፡ ከሚመ
ጡብህ ፡ ጠላቶችም ፡ ተጠበቅ ።
፲፬ የታመነ ፡ ወዳጅ ፡ እንደ ፡ ጸና ፡ አላባሽ ፡ አግሬ ፡
ነው ፡ እሱን ፡ ያገኘ ፡ ሰው ፡ ድልብ ፡ አገኘ ።
፲፭ ለታመነ ፡ ወዳጅ ፡ መለወጥ ፡ የለውም ፡ ላንደበ
ቱም ፡ መለወጥ ፡ የለውም ።
፲፮ የታመነ ፡ ወዳጅ ፡ የሚያሽር ፡ ክስ ፡ ነው ፡ (ክስ ፡
ሲያሽር ፡ ደስ ፡ እንዲያሰኝ ፡ እንደዚያ ፡ ደስ ፡
ያሰኛል ፡) እግዚአብሔርን ፡ የሚፈሩ ፡ ሰዎች ፡
ግን ፡ ያገኙታል ።
በልንጀራው ፡ እንደሱ ፡ ይሆነዋልና ፡ እግዚአ ፲፯
ብሔርን ፡ የሚፈራ ፡ ሰው ፡ ወንድሚ ፡ ወንድሚ ፡
ማለት ፡ ያቀናል ።
ልጄ ፡ በሕፃንነትህ ፡ ጥበብን ፡ ምረጣት ፡ እስከ ፲፰
ረጅም ፡ ድረስ ፡ ስትረዳህ ፡ ታገኛታለህ ።
የሚያርስ ፡ ዘርም ፡ የሚዘራ ፡ ሰው ፡ ሞፈር ፡ ፲፱
ቀምበሩን ፡ ተሸክሞ ፡ እንዲሔድ ፡ አንተም ፡
ሰውነትህን ፡ ክትት ፡ አድርገህ ፡ ወደሷ ፡ ሂድ ፡
ለሷ ፡ በመገዛት ፡ ጥቂት ፡ ትደክማለህና ፡ ፍሬ
ዋንም ፡ ፈጥነህ ፡ ትበላለህና ፡ የከበረ ፡ ፍሬዋን ፡
ጠብቅ ።
በሰነፎች ፡ ዘንድ ፡ ፈጽማ ፡ ገጣጉጥ ፡ ናት ፡ ፳
አእምሮ ፡ በሌለው ፡ ሰው ፡ ልቡናም ፡ አታድ
ርም ።
የፈተና ፡ ደንጊያ ፡ እንሥተው ፡ በተሸከሙት ፡ ፳፩
ጊዜ ፡ እንዲከብድ ፡ እንደዚሁ ፡ ትከብዳለች ፡
ፈጥኖም ፡ ይጥላታል ።
ጥበብስ ፡ እንደ ፡ ስሟ ፡ ናት ፡ ብዙ ፡ ሰዎችም ፡ ፳፪
የሚያውቋት ፡ አይደሉም ።
ልጄ ፡ ምክሬን ፡ ስማኝ ፡ በምክሬም ፡ ጸንተህ ፡ ፳፫
ኑር ፡ ምክሬን ፡ አታቃል ።
እግሮችህን ፡ ወደ ፡ ቀምበሩ ፡ አግባ ፡ (እግረ ፡ ፳፬
ልቡናህን ፡ በሥራቷ ፡ አጽና ፡) ዛንጀርዋንም ፡
በንገትህ ፡ እሠር ። (በክሣደ ፡ ልቡናህም ፡ ሥራ
ቷን ፡ ያዝ ፡)
ጫንቃህን ፡ ዝቅ ፡ አድርገህ ፡ ተሸከማት ፡ (መት ፳፭
ከፈ ፡ ልቡናህን ፡ ዝቅ ፡ አድርገህ ፡ አስባት ፡)
በግር ፡ ብረቷም ፡ አትበሳጭ ። (ሥራቷን ፡
አትሰልች ፡)
በፍጹም ፡ ሰውነትህ ፡ ወደሷ ፡ ሒድ ፡ በፍጹም ፡ ፳፮
ዕውቀትህም ፡ ሥራቷን ፡ ጠብቅ ።
ፍለጋዋን ፡ ተከተል ፡ (አምልኮቷን ፡ ጠብቅ ፡) ፳፯
ፈልጋት ፡ ታገኛታለህ ። ያዛት ፡ አትተዋት ።
ኋላ ፡ በፍጻሜ ፡ ዘመንህ ፡ ዕረፍተ ፡ ነፍስ ፡ ታገኛ ፳፰
ለህ ፡ ተድላ ፡ ደስታም ፡ ይሆንሃል ።
እግር ፡ ብረቷም ፡ እንደ ፡ ጽኑ ፡ ጋሻ ፡ ይሆንሃል ፡ ፳፱
(ሥራቷ ፡ እንደ ፡ አላባሽ ፡ አግሬ ፡ ይሆንሃል ፡)
የዘለዓለም ፡ ወርቅ ፡ በሷ ፡ ዘንድ ፡ አለና ፡ ዛን
ጀርዋም ፡ የክብር ፡ ልብስ ፡ ወደ ፡ መሆን ፡ ይመ
ለስልሃል ።
ሥራቷ ፡ ክብር ፡ ወደ ፡ መስጠት ፡ ይመለስል ፴
ሃል ፡ ማሠሪያዋም ፡ የሰማያዊ ፡ ሐር ፡ ጌጥ ፡ ይሆ
ንሃል ፡ ሥራቷ ፡ሰማያዊ ፡ ክብር ፡ ይሆንሃል ።
እንደ ፡ ምሉጣ ፡ ግምጃም ፡ ትለብሳታለህ ፡ የደ ፴፩
ስታ ፡ ዘውድንም ፡ ታቀዳጅሃለች ።
ልጄ ፡ ብልህ ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ ብትወድ ፡ ትማ ፴፪
ርም ፡ ዘንድ ፡ በልቡናህ ፡ ብትጨነቅ ።
ጥበብንም ፡ ትሰማ ፡ ዘንድ ፡ ብትወድ ፡ መከራ ፴፫
ውን ፡ ታገሥ ፡ ገርሮህ ፡ ጥበብን ፡ ትሰማ ፡ ዘንድ ፡
ብትፈልግ ።
በብዙ ፡ መምህራን ፡ ዘንድ ፡ ጸንተህ ፡ ኑር ፡ ፴፬
ከነሳቸው ፡ የተማረውን ፡ አይተህ ፡ ተከተለው ።
የመጽሐፉን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ፈጥነህ ፡ ስማ ፡ የጥ ፴፭
በብም ፡ ምሳሌ ፡ አይዘንጋህ ።

፴፮፤ የተማረ ፡ ሰው ፡ ብታይ ፡ ፈጥነህ ፡ ወደሱ ፡ ሂድ ፡
እግርህም ፡ በደጃፉ ፡ መድረክ ፡ ይመላለስ ።
፴፯፤ የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ አስብ ፡ መጻሕፍቶ
ችንም ፡ ሁለጊዜ ፡ አንብብ ፡ እሱ ፡ ልቡናህን ፡
ያጸናሃል ፡ ጥበብንም ፡ ትወዳት ፡ ዘንድ ፡ መው
ደድን ፡ ይሰጥሃል ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

፩፤ ኃጢአትን ፡ አትሥራት ፡ መከራ ፡ አያገኝህም ።
፪፤ ከበደል ፡ ራቅ ፡ እሷም ፡ ከንተ ፡ ትርቃለች ።
፫፤ ፍዳን ፡ ሰባት ፡ እጥፍ ፡ አድርገህ ፡ እንዳትቀበ
ላት ፡ በሰውነትህ ፡ ኃጢአት ፡ አትሥራ ።
፬፤ ከእግዚአብሔር ፡ መንግሥትን ፡ አትለምን ፡ ከን
ጉሥም ፡ ክብር ፡ ያለው ፡ ሹመት ፡ አትለምን ።
፭፤ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ጻድቅ ፡ ነኝ ፡ አትበል ፡
በንጉሥም ፡ ዘንድ ፡ ብልህ ፡ ነኝ ፡ አትበል ።
፮፤ ዳኛ ፡ መሆንን ፡ አትውደድ ፡ እነሆ ፡ እግዚአብ
ሔርን ፡ የበደለ ፡ ተበቅሎ ፡ ማጥፋት ፡ አትች
ልም ፡ ይሆናል ፡ እነሆ ፡ ለባለጸጋም ፡ ቃደላ ፡
ይሆናል ፡ በውነት ፡ ሥራህም ፡ ላይ ፡ ኃጢአት ፡
ትሠራለህ ።
፯፤ ያገርህንም ፡ ሰው ፡ አትበድል ፡ ራስህንም ፡ በወ
ገኖችህ ፡ መካከል ፡ አታስት ።
፰፤ ከንዲቱ ፡ ብታመልጥ ፡ አንዲቱን ፡ ከመሥራት ፡
አታመልጥምና ፡ ሁለት ፡ ኃጢአት ፡ አንድ ፡ አድ
ርገህ ፡ አትሥራ ።
፱፤ በመባዬ ፡ ብዛት ፡ እግዚአብሔር ፡ ኃጢአቴን ፡
ያስተሠርይልኛል ፡ መባም ፡ ከገባሁ ፡ ገናና ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ይቅር ፡ ይለኛል ፡ አትበል ።
፲፤ በጸለይህ ፡ ጊዜ ፡ አትቸኩል ፡ ምጽዋትን ፡ መመ
ጽወትንም ፡ አታቃል ።
፲፩፤ የሚያሳዝን ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ እግዚአብሔር ፡
አለና ፡ ባዘን ፡ ሰው ፡ አትሳቅ ።
፲፪፤ በባልንጀራህ ፡ እስትን ፡ ተግባር ፡ አታድርግ ፡
በወዳጅህና ፡ በባልንጀራህም ፡ ላይ ፡ እንዲህ ፡
አታድርግ ።
፲፫፤ ፍጻሜዋ ፡ ይጐዳሃልና ፡ በምንም ፡ በምንም ፡
ሁለጊዜ ፡ አሰትን ፡ አትውደድ ።
፲፬፤ በሊቃውንቱ ፡ መካከል ፡ አትጥቀስ ፡ ባንደበትህ ፡
የተናገርኸውን ፡ ስለትህን ፡ አትለውጥ ፡ ቃልህ
ንም ፡ አትለውጥ ።
፲፭፤ የእጅህን ፡ ሥራ ፡ ፈጣሪህም ፡ የሚያበቅልልህን ፡
ቡቃያህን ፡ ቸል ፡ አትበል ።
፲፮፤ ብዙ ፡ ናቸው ፡ ብለህ ፡ ከኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡
ጋራ ፡ አንድ ፡ አትሁን ።
፲፯፤ ሞት ፡ እንዳይቀር ፡ አስብ ፡ የኃጢአተኞች ፡
ሰዎች ፡ ፍዳቸው ፡ ዕፄሁ ፡ ዘኢይነውም ፡ እሳቱ ፡
ዘኢይጠፍዕ ፡ ያለው ፡ ነውና ፡ ሰውነትህን ፡
ፈጽመህ ፡ በንስሐ ፡ አዋርዳት ።
፲፰፤ እየነጋ ፡ ወዳጅ ፡ አትልወጥ ፡ ቀይ ፡ ወርቅ ፡ ወደህ ፡
ወዳጅህን ፡ አትጣ ።
፲፱፤ መወደዷ ፡ (ልባምነቷ ፡) ከወርቅ ፡ ይመረጣልና ፡
ብልህ ፡ ደግ ፡ የሆነች ፡ ሴትን ፡ አትጣላ ።
፳፤ በውነት ፡ በሚገዛልህ ፡ ቤተ ፡ ሰብህ ፡ ስላንተ ፡
ሰውነቱን ፡ አሳልፎ ፡ ለሞት ፡ በሚሰጥ ፡ በምን
ደኛህም ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አታድርግ ።
ብልህ ፡ ቤተ ፡ ሰብህን ፡ ከሰውነትህ ፡ ይልቅ ፡ ፳፩፤
ውደደው ፡ ነፃ ፡ ታወጣው ፡ ዘንድ ፡ ትስፋ ፡ ያደ
ረገህ ፡ ዋጋውንም ፡ አታጥፋበት ።
ሁለጊዜ ፡ ከብትህንም ፡ መፍቀድ ፡ አትተው ፡ ፳፪፤
ከነሳቸው ፡ የሚረባህንም ፡ አይተህ ፡ ለመሥዋ
ዕት ፡ አቅርብ ።
ልጆች ፡ ቢኖሩህ ፡ ምክራቸው ፡ ከሕፃንነታቸው ፡ ፳፫፤
ጀምረህ ፡ ሰቢረ ፡ ክሣድ ፡ አስተምራቸው ።
ሴቶች ፡ ልጆችም ፡ ቢኖሩህ ፡ ጠብቃቸው ፡ አታ ፳፬፤
ስቃቸው ፡ አትማቅላቸው ፡ አታብብላቸው ።
ልጅህን ፡ አቅመ ፡ሔዋን ፡ ስታደርስ ፡ አጋባት ፡ ፳፭፤
ከዚህ ፡ አስቀድሞ ፡ ጠብቃት ፡ እንዲህ ፡ ያደረ
ግህ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ታላቅ ፡ ሥራ ፡ መጨረስህ ፡
ነው ፡ ከድካምም ፡ አርፈህ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ለተ
ማረ ፡ ሰው ፡ አጋባት ።
እንደራስህ ፡ የምትወዳት ፡ ሚስት ፡ ብትኖርህ ፡ ፳፮፤
አትፍታት ።
በፍጹም ፡ ልቡናህ ፡ አባትህን ፡ አክብረው ፡ ፳፯፤
የናትህንም ፡ ምጧን ፡ አትዘንጋ ።
እነሳቸውንም ፡ ለመርዳት ፡ እንደ ፡ ተወለድህ ፡ ፳፰፤
አስብ ፡ ስላደረጉልህ ፡ ፈንታ ፡ ምን ፡ ታደርግላ
ቸዋለህ ።
በፍጹም ፡ ሰውነትህ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፍራው ፡ ፳፱፤
አገልጋዮቹ ፡ ክህናትንም ፡ አክብራቸው ።
በፍጹም ፡ እውቀትህ ፡ ፈጣሪህን ፡ ውደደው ፡ ፴፤
የሚያገለግሉት ፡ ክህናቱንም ፡ አትተዋቸው ።
እግዚአብሔርን ፡ ፍራው ፡ የሚያገለግለው ፡ ፴፩፤
ክህኑንም ፡ አክብረው ፡ የታዘዘልህ ፡ ዕድሉንም ፡
ስጠው ፡ ቀዳምያቱን ፡ ስለ ፡ ኃጢአቱ ፡ የሚሠ
ዋውን ፡ መሥዋዕት ፡ ወርቹንም ፡ ማታና ፡
ጧትም ፡ የሚሠዋውን ፡ መሥዋዕት ፡ መጀመ
ሪያ ፡ የሚወለደውንም ፡ ከብት ፡ ዋጋ ፡ ስጠው ።
ክብርህ ፡ ትበዛልህ ፡ ዘንድ ፡ ለድሀውም ፡ መጽ ፴፪፤
ውተው ።
ስለ ፡ ምጽዋትህ ፡ ሁሉ ፡ ሰውነትህ ፡ የምጽዋ ፴፫፤
ትህን ፡ ዋጋ ፡ ታገኛለች ፡ ለሞተ ፡ ሰውም ፡ ተዝ
ካር ፡ ማውጣት ፡ አትተው ።
ከሚያለቅሱ ፡ ሰዎች ፡ አትለይ ፡ ከሚያለቅሱም ፡ ፴፬፤
ሰዎች ፡ ጋራ ፡ አልቅስ ።
ሕመምተኛንም ፡ መጐብኘት ፡ ቸል ፡ አትበል ፡ ፴፭፤
በዚህ ፡ ይወዱሃል ።
በተናገርከው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ፍጻሜህን ፡ አስ ፴፮፤
ባት ፡ ሁልጊዜም ፡ አትበድል ።

## ምዕራፍ ፡ ፰ ።

በእጃቸው ፡ እንዳትወድቅ ፡ ከታላላቆች ፡ ፩፤
ሰዎች ፡ ጋራ ፡ አትከራከር ።
ቀይ ፡ ወርቅ ፡ ስለ ፡ መውደድ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ጠፍ ፪፤
ተዋልና ፡ የነገሥታቱም ፡ ልቡና ፡ ፍርድን ፡
አድልቶባቸዋልና ፡ ከባለጸጋ ፡ ጋራ ፡ አትከራ
ከር ።
ከሸፋጭ ፡ ሰውም ፡ ጋራ ፡ አትከራከር ፡ ብትከ ፫፤
ራከር ፡ ግን ፡ በእሳት ፡ ላይ ፡ እንጨት ፡ መከመ

ርሀ ፡ ነው ። ( ያ ፡ ሳይቃጠል ፡ እንዳይቀር ፡ ሳያ
ጠፋህ ፡ አይቀርም ፡ )
፬፤ እናትና ፡ አባትህን ፡ አታዋርድ ፡ ከሰነፍ ፡ ሰው ፡
ጋራ ፡ አትሳቅ ፡ አትዘበበት ።
፭፤ ስለ ፡ ኃጢአቱ ፡ የሚለማመጥን ፡ ሰው ፡ አትን
ቀፈው ፡ እኛ ፡ ሁላችንም ፡ ኃጢአተኞች ፡ እን
ደሆን ፡ አስብ ።
፮፤ ከኛ ፡ የሚያረጅ ፡ ሰው ፡ አለና ፡ በርጅናው ፡
ጊዜ ፡ ሰውን ፡ ጅጁ ፡ ጨረቱ ፡ አትበለው ።
፯፤ በሞት ፡ ሰው ፡ ደስ ፡ አይበልህ ፡ ሁላችን ፡ እን
ድንሞት ፡ አስብ ።
፰፤ የመምህራንን ፡ ነገር ፡ አታቃል ፡ ጥበብን ፡ በነሳ
ቸው ፡ ዘንድ ፡ ታገኛታለህና ፡ ምሳሌያቸውንም ፡
ተማር ። መምህራንን ፡ አገልግል ።
፱፤ የሽማግሎችን ፡ ምክራቸውን ፡ ጠብቅ ፡ እነሳ
ቸው ፡ ከባቶቻቸው ፡ ተምረዋልና ፡ አንተም ፡
ከነሳቸው ፡ ተማር ፡ በዘንክም ፡ ጊዜ ፡ የምትና
ገረውንም ፡ ታገኛለህ ፡ የምትመልሰውንም ፡
ታውቃለህ ።
፲፤ በእሳታቸው፡እንዳትቃጠል፡የኃጢአተኞችን፡
ሰዎች ፡ እሳት ፡ አትጫር ፡ በፍዳቸው ፡ እንዳ
ትጠፋ ፡ ኃጢአታቸውን ፡ አትሥራ ።
፲፩፤ በንደበቱ ፡ ነገር ፡ እንዳያስትህ ፡ ከተሳዳቢና ፡
በጠላት ፡ ዘንድ ፡ አትከራከር ።
፲፪፤ ለባለጸጋ ፡ አታበድረው ፡ ብታበድረው ፡ ግን ፡
ገንዘብህን ፡ እንዳጣህ ፡ እወቅ ።
፲፫፤ ባለጸጋውን ፡ አትዋሰው ፡ ብትዋሰው ፡ ግን ፡
እንግዴህ ፡ አንተ ፡ እንደ ፡ ከፈልህ ፡ አስብ ።
፲፬፤ እንደ ፡ ጌትነቱ ፡ መጠን ፡ ፍርድን ፡ ይለውጡለታ
ልና ፡ ከዳኛ ፡ ጋራ ፡ አትከራከር ።
፲፭፤ እንዳይቈጣብህ ፡ ከጡብጣቢ ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ መን
ገድን ፡ አትሂድ ፡ እሱ ፡ ግን ፡ ልቡ ፡ እንደወደደ ፡
ያደርጋልና ፡ አንተ ፡ በሱ ፡ስንፍና ፡ ትሞታለህ ።
፲፮፤ ከቍጡ ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ አትከራከር ፡ በፊቱ ፡ ደም ፡
ማፍሰስ ፡ እንደ ፡ ኢምንት ፡ ነውና ፡ ረዳት ፡ወደ
ሌለበት ፡ ቦታም ፡ ይወስድሃልና ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡
ወደ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ አትውጣ ።
፲፯፤ የሰማውን ፡ ነገር ፡ ማስቀረት ፡ አይችልምና ፡ ከቀ
ላል ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ አትማከር ።
፲፰፤ እንዳይደርስብህ ፡ አታውቅምና ፡ ጉዳይህን ፡ በባ
ዕድ ፡ ፊት ፡ አትናገር ።
፲፱፤ ዋጋህ ፡ እንዳይጠፋብህ ፡ ለሰው ፡ ሁሉ ፡ የልብ
ህን ፡ ምሥጢር ፡ አታውጣ ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

፩፤ ክፉ ፡ ትምርትን ፡ እንዳትማርብህ ፡ ባጠገብህ ፡
የምትተኛ ፡ ሚስትህን ፡ አታስቀናት ።
፪፤ ምሥጢርህን ፡ እንዳታወጣብህ ፡ ለሴት ፡ ልብ
ህን ፡ አትስጣት ።
፫፤ በዝሙቷ ፡ እንዳትሰነካከል ፡ የሰው ፡ ሚስት ፡
አታብብል ።
፬፤ በዘፈኗ ፡ እንዳታስትህ ፡ ከዘፋኝ ፡ ሴት ፡ ጋራ ፡
አትጫወት ።
፭፤ ፈቃዷ ፡ እንዳያስትህ ፡ ድንግልን ፡ አትቆንጥ
ጣት ።
፮፤ ርስትህን ፡ እንዳታጣ ፡ ለጋለሞታ ፡ ልቡናህን ፡
አትስጣት ።
፯፤ ምንጣኗ ፡ እንዳያስትህ ፡ የጋለሞታ ፡ መንደር ፡
አትፈልግ ።
፰፤ ከመልክ ፡ መልክም ፡ ሴት ፡ ፊትህን ፡ መልስ ፡
የጐልማሳ ፡ ሚስትም ፡ ደም ፡ ግባቷ ፡ አያስጐ
ምጅህ ፡ በሴት ፡ ደም ፡ ግባትም ፡ የሳቱ ፡ ሰዎች ፡
ብዙ ፡ ናቸው ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ፍቅሯ ፡ እንደ ፡
እሳት ፡ ይነዳል ።
፱፤ ከሰው ፡ ሚስት ፡ ጋራ ፡ አትቀመጥ ፡ ልቡና
ህን ፡ ወደሷ ፡ እንዳትወስድ ፡ ሰውነትህንም ፡
በሞት ፡ እንዳትሰነካከል ፡ በመጠጥ ፡ ጊዜ ፡ ከሷ ፡
ጋራ ፡ አትቀመጥ ።
፲፤ ድንገተኛ ፡ ወዳጅ ፡ እንደሱ ፡ አይሆንህምና ፡
የቀድሞ ፡ ወዳጅህን ፡ አትተወው ። አዲስ ፡
ወዳጅ ፡ ጉሽ ፡ ጠጅ ፡ ነው ፡ ቢከርም ፡ ግን ፡ ደስ ፡
ብሎህ ፡ ትጠጣዋለህ ።
፲፩፤ እንዲጠፉ ፡ አታውቅምና ፡ የኃጥአን ፡ ብልጽግ
ናቸው ፡ አያስቀናህ ።
፲፪፤ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ የዘነጉ ፡ ሰዎች ፡ ተድ
ላቸው ፡ አያስጐምጅህ ፡ እስኪሞቱ ፡ ድረስ ፡
እንዳይከብሩ ፡ አስብ ።
፲፫፤ ሰውነትን ፡ ከሚቀጡ ፡ ከመኳንንት ፡ ፈጽመህ ፡
ራቅ ፡ የሞት ፡ ጥርጥር ፡ አያገኝህ ፡ ሰውነትህን ፡
እንዳታጠፋ ፡ ብትቀርባቸውም ፡ ሰውነትህን ፡
እንዳታጠፋ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ በወጥመድ ፡ መካከል ፡
እንድትሄድ ፡ በገደልም ፡ መካከል ፡ እንድትመ
ላለስ ፡ እወቅ ።
፲፬፤ የተቻለህን ፡ ያህል ፡ ለባልንጀራህ ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡
ከመምህራን ፡ ጋራ ፡ ተማከር ።
፲፭፤ ጉዳይህም ፡ ከዋቆች ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ ይሁን ፡
ነገርህ ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ ይሁ
ንልህ ።
፲፮፤ ከደሀች ፡ ሰዎች ፡ በምሳሕ ፡ ይቀመጡ ፡ ምሳ
ሕም ፡ እግዚአብሔርን ፡ በመፍራት ፡ ይሁን ።
፲፯፤ ሥራው ፡ በብልሃተኛው ፡ እጅ ፡ ይከናወናል ፡
የሕዝቡንም ፡ አለቃ ፡ በቃሉ ፡ ጥበብ ፡ ያመሰ
ግኑታል ።
፲፰፤ ሸፋጭ ፡ ሰው ፡ በሀገሩ ፡ ያስፈራል ፡ ከቃሉም ፡
የተነሣ ፡ ፈጽመው ፡ ይጠሉታል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩፤ አዋቂ ፡ ንጉሥ ፡ ሠራዊቱን ፡ ይመክራል ፡
አዋቂ ፡ ዳኛም ፡ ሥራት ፡ ይሠራል ።
፪፤ ሎሌውም ፡ እንደ ፡ አለቃው ፡ ነው ፡ አገረ ፡
ገዥው ፡ እንደሚሠራው ፡ በውስጧም ፡ የሚ
ኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ይሠራሉ ።
፫፤ አላዋቂ ፡ ንጉሥ ፡ ሠራዊቱን ፡ ያጠፋል ፡ አገ
ርም ፡ በአለቆቿ ፡ ጥበብ ፡ ትጸናለች ።
፬፤ የምድር ፡ አገዛዝዋ ፡ በእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡
ነው ።
፭፤ የብልህ ፡ ሰው ፡ ጥበቡ ፡ በፊቱ ፡ ይታወቃል ።
፮፤ ስቶ ፡ በሠራው ፡ ኃጢአቱ ፡ ሁሉ ፡ ባልንጀራ
ህን ፡ አትንቀፈው ፡ ነቅፈህም ፡ ምንም ፡ ምን ፡
የምታደርገው ፡ ነገር ፡ አይኑር ።

፯ ትዕቢት ፡ በሰውና ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡
የተጠላ ፡ ነው ፡ ከሁሉም ፡ ክህደት ፡ ትከፋለች ።
፰ መንግሥትስ ፡ ስለ ፡ ክርክርና ፡ ስለ ፡ በደል ፡
ስለ ፡ ገንዘብም ፡ መውደድ ፡ ከንዱ ፡ ወገን ፡ ወዳ
ንዱ ፡ ወገን ፡ ትሄዳለች ።
፱ እንግዲህ ፡ ትቢያ ፡ አመድ ፡ የሚሆን ፡ በሕይወ
ትም ፡ ሳለ ፡ ሰውነቱ ፡ የሚተላ ፡ ሰው ፡ ለምን ፡
ይታበያል ።
፲ የሰፋ ፡ ቍስልንም ፡ በለመድኃኒት ፡ ያድነዋል ፡
ንጉሥ ፡ መበል ፡ ግን ፡ ለዛሬ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ ነገ ፡
ይሞታል ።
፲፩ ሰው ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ የትል ፡ ዕድል ፡ ይሆናል ።
፲፪ የትዕቢት ፡ መጀመሪያ ፡ ኃጢአት ፡ ሰውን ፡ ከእ
ግዚአብሔር ፡ ትለየዋለች ፡ ልቡናውንም ፡ ከፈ
ጣሪው ፡ ታስክደዋለች ።
፲፫ የኃጢአት ፡ አበጋዚ ፡ ትዕቢት ፡ ናት ፡ በጸናትም ፡
ሰው ፡ ክህደትን ፡ ታበዛበታለች ፡ ስለዚህም ፡
ነገር ፡ እግዚአብሔር ፡ የትዕቢተኞችን ፡ ፍዳ ፡
ይገልጣል ፡ ፈጽሞም ፡ ያጠፋቸዋል ።
፲፬ እግዚአብሔር ፡ ያለቆችን ፡ ዙፋን ፡ አጠፋ ፡ ስለ
ነሳቸው ፡ ፈንታ ፡ የዋህ ፡ የሆኑ ፡ ሰዎችን ፡ ሾመ ።
፲፭ እግዚአብሔር ፡ የአሕዛብን ፡ ሥራቸውን ፡ ነቀለ ፡
(አብትነታቸውን ፡) ስለነሳቸው ፡ ፈንታ ፡ የተዋ
ረዱ ፡ የሆኑ ፡ ሰዎችን ፡ አጸና ።
፲፮ እግዚአብሔር ፡ የአሕዛብን ፡ አገር ፡ አጠፋ ፡
ምድር ፡ እስከ ፡ መሆን ፡ ድረስ ፡ ስር ፡ መሠረታ
ቸውንም ፡ አጠፋ ።
፲፯ ፈጽሞ ፡ አጠፋቸው ፡ ስም ፡ አጠራራቸውንም ፡
ከዚህ ፡ ዓለም ፡ አጠፋ ።
፲፰ ትዕቢት ፡ ለሰው ፡ የተፈጠረ ፡ አይደለም ፡ ጥፋ
ትና ፡ ቍጣም ፡ ከሴት ፡ ለሚወለድ ፡ ሰው ፡ የተ
ፈጠረ ፡ አይደለም ።
፲፱ የሰው ፡ ዘር ፡ የከበረ ፡ ዘር ፡ ነው ፡ የከበረ ፡ ዘር ፡
ማነው ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈሩ ፡ ሰዎች ፡
ዘር ፡ አይደለምን ።
፳ የሰው ፡ ዘር ፡ የጐሰቈለ ፡ ዘር ፡ ነው ፡ ጐስቋላ ፡
ዘር ፡ ማነው ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ የማ
ይጠብቁ ፡ ሰዎች ፡ ዘር ፡ አይደለምን ።
፳፩ ዳኛ ፡ ከባልንጀራው ፡ ይልቅ ፡ የከበረ ፡ ነው ፡
እግዚአብሔርን ፡ የሚፈሩ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ከሱ ፡
ይልቅ ፡ ይከብራሉ ።
፳፪ የከበረውና ፡ የባለጸጋው ፡ የድሀውም ፡ ሰው ፡
መመከታቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ በመፍራት ፡
ይደረግላቸዋል ።
፳፫ ድሀውን ፡ ስለ ፡ ድህነቱ ፡ ይንቁት ፡ ዘንድ ፡ አይ
ገባም ፡ ኃጢአተኛ ፡ ሰውንም ፡ ስለ ፡ ባለጸግነቱ ፡
ያከብሩት ፡ ዘንድ ፡ አይገባም ።
፳፬ አለቆችና ፡ ነገሥታቱ ፡ መኳንንቱም ፡ ይከብ
ራሉ ፡ ከነሳቸውም ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚ
ፈራ ፡ ሰውን ፡ የሚበልጠው ፡ የለም ።
፳፭ ብልህ ፡ ቤት ፡ ሰብ ፡ በሚገባ ፡ ያገለግላል ፡
አዋቂ ፡ ሰው ፡ አይነቅፈውም ።
፳፮ ሥራህን ፡ ስትሠራ ፡ አትራቀቅ ፡ በተቸገርህበ
ትም ፡ ወራት ፡ አትኵራ ።
፳፯ መንደር ፡ ለመንደር ፡ ከሚዞር ፡ ከሚመካ ፡ ምግ
ቡንም ፡ ከማያገኝ ፡ ሰው ፡ የሚያርስ ፡ የሚቆፍር ፡
ሰው ፡ ይሻላል ።
ልጄ ፡ በየዋህነትህ ፡ ሰውነትህን ፡ ደስ ፡ አሰኛት ፡ ፳፰
የተቻለህንም ፡ ያህል ፡ አዘጋጃት ።
ራሱን ፡ የሚነፍግ ፡ ለማን ፡ቸር ፡ ይሆናል ፡ ሰው ፳፱
ነቱን ፡ የማያዘጋጃት ፡ ሰውንስ ፡ ማን ፡ ያመሰግ
ነዋል ።
ድሀውን ፡ ግን ፡ ስለ ፡ ጥበቡ ፡ ያመሰግኑታል ፡ ባለ ፴
ጠጋን ፡ ግን ፡ ስለ ፡ ባለጠግነቱ ፡ ያመሰግኑታል ።
በተቸገረ ፡ ጊዜ ፡ የሚያዝን ፡ ሰው ፡ በገንዘብ ፡ ፴፩
በተዘጋጀ ፡ ጊዜ ፡ እንዴት ፡ ደስ ፡ ይለዋል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

ድሀ ፡ በጥበቡ ፡ ይከብራል ፡ በመኳንንትም ፡ ፩
መካከል ፡ ይቀመጣል ።
መልክ ፡ መልክም ፡ ነው ፡ ብለህ ፡ ለሰው ፡ አታ ፪
ድላ ፡ መልክ ፡ ጥፉ ፡ ነው ፡ ብለህ ፡ ሰውን ፡ አት
ናቀው ።
ንብ ፡ ከወፎች ፡ ሁሉ ፡ በመልክ ፡ ትከፋለች ፡ ፫
ማሯ ፡ ግን ፡ ከሁሉ ፡ ይጣፍጣል ።
በልብስህ ፡ ጌጥ ፡ አትታበይ ። የእግዚአብሔር ፡ ፬
ሥራው ፡ ልዉጥ ፡ ምሥጢሩም ፡ ከሰው ፡ የተ
ሠወረ ፡ ነውና ። በከበርህበት ፡ ወራት ፡ ራስ
ህን ፡ አታኵራ ።
በዚህ ፡ ዓለም ፡ በመከራ ፡ የወደቁ ፡ መኳንንት ፡ ፭
ብዙ ፡ ናቸው ፡ ዘውድ ፡ የተቀዳጀ ፡ በሕታዊም ፡
አለ ።
ፈጽመው ፡ የጐሰቈሉ ፡ መኳንንት ፡ ብዙ ፡ ናቸው ፡ ፮
በጠላታቸውም ፡ እጅ ፡ የወደቁ ፡ መኳንንት ፡
ብዙ ፡ ናቸው ።
ሳትመረምረው ፡ አትንቀፈው ፡ አስቀድመህ ፡ ፯
ነገሩን ፡ ጠይቀው ፡ ኋላ ፡ ትቈጣዋለህ ።
ሳትሰማ ፡ አትመልስ ፡ በሰው ፡ ነገርም ፡ አትግባ ። ፰
ግዳጅህም ፡ ባልሆነ ፡ ነገር ፡ እልፍ ፡ እልፍ ፡ ብለህ ፡ ፱
አትናገር ፡ ይሙት ፡ በቃ ፡ በተፈረደበት ፡
ሰውም ፡ ቆመህ ፡ አትከራከር ።
ሥራህን ፡ ካበዛህ ፡ ትከብር ፡ ዘንድ ፡ አያሠለጥን ፲
ህምና ፡ ልጄ ፡ ሥራህን ፡ አታብዛ ፡ ፈጥነህም ፡
ብትሠራ ፡ ከችጋር ፡ አታመልጥም ፡ ብትከተላ
ትም ፡ ብዕልን ፡ አታገኘትም ።
በመከበር ፡ የሚቸኩል ፡ ፈጽሞም ፡ የሚደክም ፡ ፲፩
የሚቸገር ፡ አለና ፡ ብትከተላት ፡ ብዕልን ፡ አታ
ገኛትም ።
ደክሞ ፡ ሳለ ፡ የማይለምን ፡ ምንም ፡ ምን ፡ ማድ ፲፪
ረግ ፡ ሳይችል ፡ የሚገዛ ፡ አለ ፡ ምን ፡ ቢጸና ፡
ፈጽሞ ፡ የሚቸገር ፡ አለ ። እግዚአብሔር ፡ ግን ፡
በይቅርታ ፡ ዓይን ፡ ቢያየው ፡ ከችጋሩ ፡ ለይቶ ።
ያገነዋል ፡ ያከብረዋል ፡ ብዙ ፡ ሰዎችም ፡ ያደን ፲፫
ቁታል ።
ደዌና ፡ ጥዒና ። ፲፬
ሞትና ፡ ሕይወት ። ፲፭
ብልጽግናና ፡ ችጋር ፡ መገኛቸው ፡ ከእግዚአብ ፲፮
ሔር ፡ ዘንድ ፡ ነው ።
የእግዚአብሔር ፡ ረድኤቱ ፡ ደጋግ ፡ ሰዎችን ፡ ፲፯
ትጠብቃቸዋለች ፡ ፈቃዱም ፡ ዓለም ፡ ደስ ፡ ያሰኘዋል

፲፰ እየነፈገ ፡ በንፍገቱ ፡ ብዙት ፡ የሚከብር ፡ ሰው ፡
አለ ። በዚችም ፡ በንፍገቱ ፡ ተድላ ፡ ደስታውን ፡
ይፈጽምበታል ።
፲፱ ያርፍ ፡ ዘንድ ፡ ተስፋ ፡ በደረገ ፡ ጊዜ ፡ እበላለሁ ፡
እጠጣለሁ ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ እንግዴህስ ፡ ደስ ፡ ይለ
ኛል ፡ ገንዘብም ፡ በቃኝ ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ የሚሞትብ
ትን ፡ ቀን ፡ አያውቅም ፡ ገንዘቡን ፡ ሁሉ ፡ ለባ
ዕድ ፡ ትቶ ፡ እሱ ፡ ይሞታል ።
፳ እግዚአብሔርን ፡ በመፍራት ፡ ጸንተህ ፡ ኑር ፡
በገንዘብህም ፡ እውቀት ፡ በሥራህም ፡ ጸንተህ ፡
እንድታረጅ ፡ ሁን ።
፳፩ የኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ ሥራቸው ፡ አያስጎም
ጅህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ እመን ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡
ሊያደርገው ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡
ቀሊል ፡ ነውና ፡ ድኃውን ፡ ድንገት ፡ ያከብረ
ዋል ፡ ድካምህን ፡ ተስፋ ፡ አድርገው ።
፳፪ የእግዚአብሔር ፡ በረከት ፡ ለደጋጎች ፡ ሰዎች ፡
ዋጋቸው ፡ ናት ፡ የደግ ፡ ሰውም ፡ በረከቱ ፡ ትበ
ዛለች ።
፳፫ ዋጋ ፡ የለኝምና ፡ እንግዴህ ፡ ወዲህ ፡ ወዳጅ ፡
አልወድም ፡ አትበል ።
፳፬ እንግዴህስ ፡ ገንዘብ ፡ በቃኝ ፡ አልቸገርም ፡ አት
በል ።
፳፭ ለሰው ፡ እንደ ፡ ሥራው ፡ ዋጋውን ፡ የሚከፍ
ለው ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የሞት ፡ ቀን ።
፳፮ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ቀሊል ፡ ነውና ፡ በሕ
ይወት ፡ ጊዜ ፡ ሞትን ፡ በሞትም ፡ ጊዜ ፡ ሕይወ
ትን ፡ ይዘነጓታል ።
፳፯ ክፉ ፡ ቀን ፡ ልትመጣ ፡ አስቀድሞ ፡ ጥጋብ ፡ ያቀ
ናጣል ፡ የሰው ፡ ሥራውም ፡ በፍጻሜ ፡ ዘመኑ ፡
ይታወቃል ።
፳፰ ፍጻሜውን ፡ ሳታይ ፡ ሰውን ፡ ደግ ፡ ሰው ፡ አትበ
ለው ፡ የሰው ፡ እንዋወሩ ፡ በልጆቹ ፡ ይታወቃል ።
፳፱ ተንኰለኛ ፡ ብዙ ፡ ይተንኰልብሃልና ፡ ያገኘኸ
ውን ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ቤትህ ፡ አታግባ ።
፴ ቆቅ ፡ በበቀለ ፡ ቡቃያ ፡ በወጥመድ ፡ ይያዛል ፡ የት
ዕቢተኛም ፡ ሰው ፡ ልቡ ፡ እንደዚሁ ፡ በትዕቢት ፡
ይያዛል ፡ መከራውንም ፡ እንደ ፡ ጉበኛ ፡ ይመለ
ከታታል ።
፴፩ ተንኰለኛ ፡ ሰው ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ ያደረግህለትን ፡
ያህል ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ይከፍልሃል ፡ ነቀፋ ፡ ሳይኖ
ርብህ ፡ ነቀፋ ፡ ያወጣልሃል ።
፴፪ በእሳት ፡ ትንታግ ፡ ብዙት ፡ ፍሙ ፡ ይበዛል ፡ ኃጢ
አተኛ ፡ ሰውም ፡ ኃጢአት ፡ ሠርቶ ፡ ሰውነቱን ፡
ያጠፋታል ።
፴፫ ክፉ ፡ ነገርን ፡ ይሠራብሃልና ፡ ሁለጊዜ ፡ ስድ
ብን ፡ እንዳያደርግብህ ፡ ከክፉ ፡ ሰው ፡ ተጠበቅ ።
፴፬ ባዕድ ፡ ሰውን ፡ ከንተ ፡ ጋራ ፡ ብታሳድር ፡ ያው
ክሃል ፡ ይወነጅልሃል ፡ ከገንዘብህ ፡ ይለይሃል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

፩ በጎ ፡ ሥራ ፡ በሠራህ ፡ ጊዜ ፡ የበጎነትህን ፡
ዋጋ ፡ በምታገኝ ፡ ገንዘብ ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ የምት
ሠራለትን ፡ እወቅ ።
ለውነተኛ ፡ ሰው ፡ ሥራህን ፡ ሥራ ፡ ዋጋህን ፡ ፪
ታገኛለህ ፡ በሱ ፡ ዘንድ ፡ በታገኘው ፡ በፈጣሪው ፡
ዘንድ ፡ ዋጋህን ፡ ታገኛለህ ።
ኃጢአትን ፡ በሚሠራ ፡ ምጽዋትንም ፡ በማይመ ፫
ጸውት ፡ ሰው ፡ ዘንድ ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ የለም ።
በለጸጋ ፡ እንዳይወስድብህ ፡ ለድሀ ፡ ሰው ፡ ምጽ ፬
ዋትህን ፡ ስጥ ።
ለድሀ ፡ ሰው ፡ ምጽዋትን ፡ ስጥ ፡ ለባለጸጋ ፡ ግን ፡ ፭
አትስጥ ፡ ገንዘብህን ፡ እሱ ፡ እንዳይወስድብህ ፡
ገበታህን ፡ አጥብት ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ ስላደረግህ
ለት ፡ ፈንታ ፡ በሱ ፡ ዘንድ ፡ ክፋትን ፡ እጥፍ ፡
ሆና ፡ ታገኛታለህና ፡ በገንዘብህም ፡ ድል ፡ እንዳ
ይነሣህ ፡ ገበታህን ፡ አጥብት ።
እግዚአብሔር ፡ ኃጢአተኞች ፡ ሰዎችን ፡ ይጠ ፮
ላቸዋልና ፡ ክፉ ፡ ሰዎችንም ፡ ተበቅሎ ፡ ያጠፋ
ቸዋልና ።
ለኃጢአተኛ ፡ ከትሰጥ ፡ ለድሀ ፡ ሰው ፡ ስጥ ፡ ፯
ተድላ ፡ ደስታም ፡ በደረግህ ፡ ጊዜ ፡ ወዳጅህ ፡ አያ
ምልጥህ ።
በመከራህ ፡ ጊዜ ፡ ጠላትህ ፡ አይሠወርህ ። ፰
ተድላ ፡ ደስታህ ፡ ጠላቶችህን ፡ ያሳዝናቸዋል ፡ ፱
ችጋርህም ፡ ወዳጆችህን ፡ አስወጥቶ ፡ ይሰዳቸ
ዋል ።
የልቡናው ፡ ክፋት ፡ እንደ ፡ ብረት ፡ ዝገት ፡ ነውና ፡ ፲
ጠላትህን ፡ ፈጽመህ ፡ አትመነው ።
ብትቸገርም ፡ ሳይወድህ ፡ ያገለግልሃል ፡ ሰውነ ፲፩
ትህን ፡ አጽናት ፡ ተጠበቅበት ፡ በዜቃዋ ፡ እንደ ፡
ረገፈ ፡ መስተዋትም ፡ ትሆንበታለህ ፡ ፈጽሞም ፡
አይችልህም ።
እንዳይጎዳህ ፡ በጠጉብህ ፡ አታቁመው ፡ በቦታ ፲፪
ህም ፡ አይቀመጥ ፡ ሹመትህንም ፡ እንዳይወስ
ድብህ ፡ አታሠልጥነው ፡ ኋላ ፡ በፍጻሜ ፡ ዘመ
ንህ ፡ ቃሌን ፡ ታውቀው ፡ ዘንድ ፡ አለህ ፡ ምክ
ሬንም ፡ ታስበዋለህ ።
ለምድር ፡ እባብ ፡ ለክፉ ፡ አውሬስ ፡ ሁሉ ፡ መን ፲፫
ከስን ፡ ማን ፡ ያስተምረዋል ።
ከኃጢአተኛም ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ የሚኖር ፡ እንደ ፲፬
ዚሁ ፡ ነው ፡ በኃጢአቱም ፡ አንድ ፡ ይሆ
ናል ።
ጠላትህ ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ይቆማል ፡ ፲፭
ነገር ፡ ግን ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ እስክትመለስ ፡ ድረስ ፡
አታየውም ፡ ካንተም ፡ ጋራ ፡ መከራውን ፡ አይ
ታገሥም ።
በከንፈሩ ፡ ጠላትህ ፡ ቃሉን ፡ ያጣጥምልሃል ፡ ፲፮
በልቡ ፡ ግን ፡ በጉድጓድ ፡ ይጥልህ ፡ ዘንድ ፡ ይመ
ክራል ፡ ጠላትህ ፡ በይኑ ፡ ያለቅስልሃል ፡ ከሳ
ተህ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ከደምህ ፡ ( ቢያማህ ፡ ቢያ
ማህ ፡ ) አይጠግብም ።
ብትቸገርም ፡ ከሁሉ ፡ አስቀድሞ ፡ በፊትህ ፡ ፲፯
ታገኘዋለህ ፡ የሚረዳህ ፡ መስሎ ፡ ራሱን ፡ አዋ
ርዶ ፡ በእግርህ ፡ በታች ፡ ይሰግዳል ።
በእጁ ፡ ያጨበጭባል ፡ ራሱን ፡ ይነቀንቃል ፡ ፲፰
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ፊቱን ፡ መልሶ ፡ ይጠቃቀ
ስብሃል ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

፩ አደሮ ፡ ማር ፡ የዳሰሰ ፡ ሰው ፡ በሱ ፡ ይያዝል ፡
ትዕቢተኛ ፡ ሰውንም ፡ ወዳጅ ፡ ያደረገ ፡ ሰው ፡
እንደሱ ፡ ይሆናል ።
፪ የከበደ ፡ ሸክምን ፡ እንሥተህ ፡ በራስህ ፡ አትሸ
ከም ፡ ገንዘብህንም ፡ ከሚበረታብህ ፡ ከባለጸጋ ፡
ገንዘብ ፡ ጋራ ፡ አትጨምር ፡ የሸክላ ፡ ጉልቻ ፡
ከብረት ፡ ድስት ፡ ጋራ ፡ በየት ፡ አንድ ፡ ይሆናል ፡
እሷ ፡ መትቻ ፡ እሷ ፡ ትጮኻለችና ፡ እሷም ፡
ትሰብራለችና ።
፫ እንደዚህ ፡ ሁሉ ፡ ባለጸጋ ፡ እሱ ፡ ይበድላል ፡
እሱ ፡ ይቈጣል ፡ ድሀ ፡ ግን ፡ እሱ ፡ ይለማመጣል ።
፬ የምትጠቅመው ፡ ነገር ፡ ቢኖር ፡ ወደሱ ፡ ያቀር
ብሃል ፡ ብትቸገር ፡ ግን ፡ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ አያ
ይህም ።
፭ ገንዘብ ፡ ቢኖርህ ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ይሆናል ፡
ገንዘብህንም ፡ ይጨርስልሃል ፡ ዳግመኛም ፡ አያ
መሰግንህም ።
፮ የሚያዝነው ፡ ኃዘን ፡ ቢኖር ፡ ያባብልሃል ፡ ብዙ ፡
ተስፋም ፡ ይሰጥሃል ፡ ይስቅልሃል ፡ በጎ ፡ ነገርም ፡
ይናገርሃል ፡ ምን ፡ ትወዳለህ ፡ ይልሃል ።
፯ በመብሉም ፡ ይሸነግልሃል ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ሁለት ፡
ጊዜ ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ ያስትሃል ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡
እንዳይሰማህ ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ ይመለሳል ፡ ቢያይ
ህም ፡ ይስቅብሃል ፡ ራሱን ፡ ይነቀንቅብሃል ።
፰ እንዳያስትህ ፡ እንዳያታልልህ ፡ ከንዲህ ፡ ያለ ፡
ሰው ፡ ተጠበቅ ፡ በተድላ ፡ በደስታህም ፡ መከ
ከል ፡ ኃዘን ፡ አታግባ ።
፱ ባለጸጋ ፡ ያዘዘህን ፡ ለጊዜው ፡ እሺ ፡ በለው ፡ ቢጠ
ራህም ፡ እምቢ ፡ አትበለው ፡ ፈጽሞ ፡ ይወድሃል ።
፲ አትራቅ ፡ አትሳት ፡ ነገር ፡ ግን ፡ እንዳይዘነጋህ ፡
ፈጽመህ ፡ አትራቀው ።
፲፩ ከሱም ፡ ጋራ ፡ ነገር ፡ አታብዛ ፡ በነገሩ ፡ ብዛት ፡
ይፈትንሃልና ፡ ካንተም ፡ ጋራ ፡ የሚስቅ ፡ መስሎ ፡
ይመረምርሃልና ፡ በነገሩ ፡ ብዛት ፡ አትመነው ።
፲፪ መታሠሩ ፡ ጥፋቱ ፡ አያሳዝነውምና ፡ የባልንጀ
ራውን ፡ ምክር ፡ ለሚያወጣ ፡ ሰው ፡ ይቅርታ ፡
የለውም ።
፲፫ ከገዳይህ ፡ ጋራ ፡ ትሔዳለህና ፡ እወቅ ፡ አጥብ
ቀህ ፡ ተጠበቅ ።
፲፬ ከብት ፡ ሁሉ ፡ ዘመዱን ፡ ይወዳል ፡ ሰውም ፡ ሁሉ ፡
ባልንጀራውን ፡ ይወዳል ።
፲፭ ፍጥረቱ ፡ ሁሉ ፡ እንደሱ ፡ ካለ ፡ ፍጥረት ፡ ጋራ ፡
አንድ ፡ ይሆናል ፡ ሰውም ፡ የሚመስለውን ፡ ይከ
ተላል ።
፲፮ ተኵላ ፡ ከበግ ፡ ጋራ ፡ በየት ፡ ወዳጅ ፡ ይሆናል ፡
እንደዚሁስ ፡ ሁሉ ፡ ኃጢአተኛ ፡ ሰው ፡ ከጻ
ድቅ ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ በየት ፡ ወዳጅ ፡ ይሆናል ።
፲፯ ውሾችን ፡ ከጅቦች ፡ ጋራ ፡ ማን ፡ ያስማማቸ
ዋል ፡ ድሀውንስ ፡ ከባለጸጋው ፡ ጋራ ፡ ማን ፡
ወዳጅ ፡ ያደርገዋል ።
፲፰ እንደዚሁም ፡ ሁሉ ፡ ባለጸጋው ፡ ድሀውን ፡
ይቀማዋል ።
ትዕቢተኛ ፡ ሰው ፡ ራሱን ፡ የሚያዋርደውን ፡ ፲፱
ሰው ፡ ይጸየፈዋል ፡ እንደዚሁም ፡ ሁሉ ፡ ባለጸ
ጋው ፡ ድሀውን ፡ ይጸየፈዋል ።
ባለጸጋ ፡ ቢፍገመገም ፡ ወዳጆቹ ፡ ይደግፉታል ፡ ፳
ድሀ ፡ ግን ፡ ቢወድቅ ፡ ባልንጀሮቹ ፡ ይረግጡ
ታል ።
ባለጸጋ ፡ ቢያድጠው ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ያነሡታል ፡ ፳፩
ቢናገርም ፡ ነገሩን ፡ ያቀኑለታል ፡ ድሀ ፡ ግን ፡
ቢስት ፡ ይረግሙታል ፡ በጎ ፡ ነገርም ፡ ቢናገር ፡
አያደምጡትም ።
ባለጸጋ ፡ ቢናገር ፡ ሁሉ ፡ ዝም ፡ ይላል ፡ ቃሉ ፡ ፳፪
ንም ፡ ያደንቁለታል ፡ ነገሩንም ፡ እስከ ፡ ደመና ፡
ያደርሱለታል ፡ ድሀ ፡ ግን ፡ ምን ፡ በጎ ፡ ነገር ፡
ቢናገር ፡ ይህ ፡ ምንድነው ፡ ይሉታል ፡ ቢሰነካከ
ልም ፡ ያዳፉታል ።
ኃጢአት ፡ ሳትሠራ ፡ ባለጸግነት ፡ ደግ ፡ ነው ፡ ፳፫
ደሀ ፡ ችጋሩን ፡ በፉ ፡ ያከፋፋታል ።
ደስም ፡ ቢለው ፡ ቢያዝንም ፡ የሰው ፡ ልቡ ፡ ፳፬
ፊቱን ፡ ይለውጠዋል ።
ደስ ፡ ያለው ፡ ልቡና ፡ ምልክቱ ፡ ብሩህ ፡ ገጽ ፡ ፳፭
ነው ፡ ደክመህ ፡ የጥበብን ፡ ምክር ፡ ታገኛለህ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

በፉ ፡ ያልተሰነካከለ ፡ ሰው ፡ የተደነቀ ፡ ነው ። ፩
ኃጢአተኛ ፡ ሰውን ፡ ግን ፡ መንፈሳዊ ፡ ኃዘን ፡
አያስደነግጠውም ።
ኃጢአት ፡ ሠርቶ ፡ ሰውነቱን ፡ የሚያሳዝን ፡ ፪
አለኝታውንም ፡ የሚያጣ ፡ ሰው ፡ የተደነቀ ፡
ነው ።
ነገር ፡ ለማያውቅ ፡ ሰው ፡ ሹመት ፡ አይገባውም ፡ ፫
ለንፉግም ፡ ሰው ፡ ገንዘብ ፡ አይገባውም ።
ሰውነቱን ፡ የሚነፍጋት ፡ ሰው ፡ ለሌላ ፡ ሰው ፡ ፬
ያከማቻል ፡ ሌላ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ በገንዘቡ ፡ ደስ ፡
ይለዋል ።
ሰውነቱን ፡ የሚነፍግ ፡ በገንዘቡም ፡ ደስ ፡ የማ ፭
ይለው ፡ ሰው ፡ ለማን ፡ ይሰጥ ፡ ዘንድ ፡ አለው ።
ሰውነቱን ፡ ከሚነፍግ ፡ ሰው ፡ የሚከፋ ፡ የለም ፡ ፮
ለክፋቱም ፡ እሱ ፡ ፍዳ ፡ ይሆነዋል ።
በጎ ፡ ሥራም ፡ ቢያደርግ ፡ ባረጀ ፡ ጊዜ ፡ ብቻ ፡ ፯
ነው ፡ ኋላም ፡ ኃጢአቱ ፡ ይገለጣል ።
የንፉግ ፡ ሰው ፡ ዓይኑ ፡ ክፉ ፡ ነው ፡ ከድሀ ፡ ፰
ፊቱን ፡ የሚመልስ ፡ ሰውነቱን ፡ ቸል ፡ ይላል ።
ለስሱ ፡ ሰው ፡ ዓይን ፡ እድሉ ፡ አያጠግበውም ፡ ፱
የልቡናውም ፡ ንፍገት ፡ ሰውነቱን ፡ ያከሳዋል ።
የንፉግ ፡ ሰው ፡ ዓይኑ ፡ እህል ፡ ይነፍጋል ፡ በማ ፲
ዕድም ፡ ይነፍጋል ።
ልጄ ፡ የሚቻልህን ፡ ያህል ፡ ሰውነትህን ፡ አዘጋ ፲፩
ጃት ፡ በሚገባህ ፡ ገንዘብ ፡ ለእግዚአብሔር ፡
መባ ፡ አግባ ።
ሞት ፡ እንዳይቀር ፡ አስብ ፡ የምትሞትበትም ፡ ፲፪
ቀን ፡ ትቀራለች ፡ ብለህ ፡ አታጠራጥርህ ።
ሳትሞት ፡ ለባልንጀራህ ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ አድርግ ፡ ፲፫
እጅህንም ፡ ዘርግተህ ፡ የተቻለህን ፡ ያህል ፡ ስጥ ።
በተድላህ ፡ በደስታህ ፡ ጊዜ ፡ እንዳትታጣ ፡ ሁን ፡ ፲፬

በነ ፡ አድልም ፡ አያምልጥህ ።
፲፭ ገንዘብህን ፡ ለባዕድ ፡ ትተዋለህና ፡ ወራሾችህ ፡
ገንዘብህን ፡ ሁሉ ፡ ይከፈላሉ ።
፲፮ ገንዘብህን ፡ እንሥትህ ፡ ስጥ ፡ በመቃብር ፡ የም
ታገኘው ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ የለምና ፡ ሰውነት
ህን ፡ ደስ ፡ አሰኛት ።
፲፯ ሕግ ፡ ቢያፈርሱ ፡ ሞት ፡ ተፈጥሯልና ፡ ሰው ፡
ሁሉ ፡ እንደ ፡ ልብስ ፡ ይጠፋል ።
፲፰ ቅጠሉ ፡ ጭፍቅ ፡ ያለ ፡ የእንጨት ፡ ቅጠል ፡ የመ
ጀመሪያው ፡ ቅጠል ፡ እንዲረግፍ ፡ ደማዊና ፡
ሥጋዊ ፡ ፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ እንዲሁ ፡ ነው ፡ ይህ ፡
ይወለዳል ፡ ያ ፡ ይሞታል ።
፲፱ ሥራው ፡ ሁሉ ፡ ፈጽሞ ፡ ይጠፋል ፡ ሠሪውም ፡
ከሥራው ፡ ጋራ ፡ ይጠፋል ።
፳ ነገር ፡ ግን ፡ ንስሐ ፡ ገብቶ ፡ የሞተ ፡ ሕጉንም ፡
የጠበቀ ፡ በገንዘቡም ፡ ያወቀበት ፡ ሰው ፡ የተደ
ነቀ ፡ ነው ።
፳፩ የጥበብን ፡ ሥራዋን ፡ በልቡ ፡ የሚያስብ ፡ ምሥ
ጢሯንም ፡ የተማረ ፡ ሰው ፡ የተደነቀ ፡ ነው ።
፳፪ ጥበብን ፡ ተከተላት ፡ ምሥጢሯንም ፡ መርምር ፡
ሥራቷንም ፡ ጠብቅ ።
፳፫ መስኮቷን ፡ የሚጐበኝ ፡ በደበበይዎቿም ፡ ተቀ
ምጦ ፡ የሚያዳምጥ ።
፳፬ በቤቷም ፡ አጠገብ ፡ የሚኖር ፡ በዙሪያዋም ፡ የድ
ንኳኑን ፡ ካስማ ፡ የሚተክል ።
፳፭ ሰውነቱን ፡ በሥልጣኗ ፡ የምያስጠብቅ ፡ በማረ ፡
ማደሪያዋም ፡ የሚኖር ።
፳፮ ልጆቹንም ፡ በረድኤቷ ፡ የሚያስጠብቅ ፡ በዘ
ጠኑም ፡ ሕገጋት ፡ ጸንቶ ፡ የሚኖር ።
፳፯ በሷም ፡ ከመከራው ፡ የሚያርፍ ፡ በክብሯም ፡
ጸንቶ ፡ የሚኖር ፡ ሰው ፡ የተደነቀ ፡ ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈራ ፡ ሰው ፡ እንዲህ ፡
ያደርጋል ፡ ሕጉንም ፡ የሚጠብቅ ፡ ሰው ፡ ያገኘ
ታል ።
፪ እንደናቱ ፡ ትከባከበዋለች ፡ እንደ ፡ ቆንጆ ፡
ሴትም ፡ ትዋሐደዋለች ።
፫ የጥበብን ፡ እህል ፡ ትመግበዋለች ፡ የእውቀት
ንም ፡ ውኃ ፡ ታጠጣዋለች ።
፬ የሚጠብቃት ፡ ሰው ፡ በመከራ ፡ አይወድቅም ፡
የሚታመንባትም ፡ ሰው ፡ አያፍርም ።
፭ ከባልንጀራው ፡ ይልቅ ፡ ታገነዋለች ፡ በብዙ ፡
ሰዎች ፡ መካከልም ፡ ነገር ፡ ይናገራል ።
፮ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ትሰጠዋለች ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡
ያለበት ፡ ዘውድንም ፡ ታቀዳጀዋለች ፡ ስሙንም ፡
ለዘለዓለሙ ፡ ያስጠራል ።
፯ ሰነፎች ፡ ግን ፡ አያገኟትም ፡ ኃጢአተኞች ፡ ሰዎ
ችም ፡ አያዩትም ።
፰ ከትዕቢተኞችም ፡ ሰዎች ፡ የራቀች ፡ ናት ፡ አሰ
ተኞችም ፡ አያስቧትም ።
፱ እግዚአብሔርን ፡ በመፍራት ፡ የሚናገር ፡ አይ
ደለምና ፡ ኃጢአተኛ ፡ ሰው ፡ ባንደበቱ ፡ የተና
ገረው ፡ ነገር ፡ ያማረ ፡ አይደለም ።
ምሳሌን ፡ በጥበብ ፡ ይናገራታል ፡ እግዚአብሔ ፲
ርም ፡ የሚማራትን ፡ ሰው ፡ ይረዳዋል ።
ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ብዬ ፡ከሥጋ ፡ከጠፎ ፡ ተከለ ፲፩
ከልሁ ፡ አትበል ፡ እሱ ፡ የጠላውንም ፡ አትሥራ ።
ኃጢአት ፡ ሠርተህ ፡ እሱ ፡ አሳተኝ ፡ አትበል ፡ ፲፪
እግዚአብሔር ፡ የረከሰውን ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ጠል
ቷልና ፡ እሱስ ፡ ኃጢአተኛ ፡ ሰውን ፡ አይወድም ።
የሚፈሩትንም ፡ ሰዎች ፡ ይወዳቸዋል ። ፲፫
እሱ ፡ ቀድሞ ፡ ሰውን ፡ በንጽሐ ፡ ጠባይዕ ፡ ፲፬
ፈጥሮ ፡ በወደደው ፡ ሥራው ፡ ተወው ።
ትእዛዙን ፡ ትጠብቅ ፡ ዘንድ ፡ ሃይማኖቱንም ፡ ፲፭
ታጸና ፡ ዘንድ ፡ ብትወድ ፡ ግን ፡ ፈቃዱ ፡ ነው ።
እጅህን ፡ በመረጥኸው ፡ ትጨምር ፡ ዘንድ ፡ ፲፮
እነሆ ፡ እሳትና ፡ ውኃን ፡ አኖረልህ ። ( ጽድቅና ፡
ኃጢአትን ፡ )
ሞትና ፡ ሕይወትም ፡ በሰው ፡ ፊት ፡ ነው ፡ ከነሳ ፲፯
ቸው ፡ የመረጠውን ፡ ሥላሴ ፡ ይሰጡታል ።
የእግዚአብሔር ፡ ጥበቡ ፡ ብዙ ፡ ነውና ፡ ዕውቀ ፲፰
ቱም ፡ የጸና ፡ ነውና ፡ ሁሉን ፡ ያውቃል ፡ ሁሉን ፡
ያያል ።
ዓይኖቹም ፡ የሚፈሩትን ፡ ሰዎች ፡ ይመለከታሉ ፡ ፲፱
እሱም ፡ የሰውን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ያውቃል ።
ኃጢአት ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ እሱስ ፡ ያዘዘው ፡ ፳
የለም ፡ ይበድልም ፡ ዘንድ ፡ ማንም ፡ ማን ፡ አላ
ሰናበታውም ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

ጥቅም ፡ የሌላቸው ፡ ብዙ ፡ ልጆችን ፡ አትው ፩
ደድ ፡ በክፉ ፡ ልጆችም ፡ ደስ ፡ አይበልህ ።
በነሳቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ ከሌለ ፪
ባቸው ፡ ቢበዙም ፡ በነሳቸው ፡ ደስ ፡ አይበልህ ።
በሕያንነትም ፡ ሳሉ ፡ አትመናቸው ፡ ብዛታቸ ፫
ውም ፡ ደስ ፡ አያሰኝህ ። ከሺህ ፡ ልጆች ፡
አንድ ፡ አዋቂ ፡ ልጅ ፡ ይሻላል ፡ ክፉ ፡ ልጅም ፡
ከመውለድ ፡ ሳይወልዱ ፡ መሞት ፡ ይሻላል ።
አዋቂ ፡ በሆነ ፡ ባንድ ፡ ልጅ ፡ አገር ፡ ትጸናለ ፬
ችና ፡ በኃጢአተኞች ፡ ልጆች ፡ ብዛት ፡ ግን ፡
ጥፋት ፡ ትጠፋለችና ፡ ክፉ ፡ ልጅ ፡ ከመውለድ ፡
ሳይወልዱ ፡ መሞት ፡ ይሻላል ።
ዓይኔ ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ብዙ ፡ ነገር ፡ አየች ። ከዚ ፭
ህም ፡ የሚበልጥ ፡ ነገሮዬ ፡ ሰማች ።
በኃጢአተኞች ፡ ወገኖች ፡ መቅሠፍት ፡ ትመ ፮
ጣለች ፡ በወንጀለኞችም ፡ ወገኖች ፡ ጥፋት ፡
ትመጣለች ።
በኃይላቸው ፡ የታመኑ ፡ የቀደሙ ፡ አርበኞ ፯
ችም ፡ ሰውነታቸውን ፡ አላዳኑም ።
ሎጥ ፡ ለኖረባቸው ፡ ራሳቸውን ፡ ላኩሩ ፡ ሎጥ ፰
ንም ፡ ላስጸየፉት ፡ አገሮች ፡ አልራራላቸውም ።
በኃጢአታቸው ፡ ጠፉ ፡ እንጂ ፡ ኃጢአተኞች ፡ ፱
ወገኖችንም ፡ ይቅር ፡ አላላቸውም ።
የተሰበሰቡ ፡ ልቡናቸውንም ፡ ያከፉ ፡ እነዚህ ፡ ፲
ስሳ ፡ እልፍ ፡ አርበኞች ፡ ናቸው ።
ክሣደ ፡ ልቡናውን ፡ ያጸና ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ፲፩
ቢኖር ፡ እሱ ፡ ቢድን ፡ ድንቅ ፡ ነው ፡ ይቅርታ ፡

መቅሠፍት ፡ ከሱ ፡ ዘንድ ፡ ይመጣልና ፡ ይቅር ፡
ማለት ፡ ይችላል ፡ መቅሠፍትንም ፡ ማምጣት ፡
ይችላል ።
፲፪ ቍጣው ፡ እንደ ፡ ቸርነቱ ፡ ብዛት ፡ መጠን ፡
ነው ፡ ሰውንም ፡ እንደ ፡ ሥራው ፡ ይከፍለዋል ።
፲፫ ኃጢአተኛ ፡ ሰው ፡ ከመከራ ፡ አያመልጥም ፡
ደግ ፡ ሰውም ፡ የትዕግሥቱን ፡ ዋጋ ፡ አያጣም ።
፲፬ ምጽዋት ፡ ሁሉ ፡ ይቅርታን ፡ ያመጣል ፡ ሰውም ፡
እንደ ፡ ሥራው ፡ ዋጋውን ፡ ያገኛል ።
፲፭ ኃጢአት ፡ ሠርተህ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ አመል
ጣለሁ ፡ በሰማያትም ፡ የሚያገኘኝ ፡ የለም ።
፲፮ በብዙ ፡ አሕዛብም ፡ ዘንድ ፡ የሚያውቀኝ ፡ የለም ።
፲፯ የሰውነቴስ ፡ ቍጥሯ ፡ ለዓለሙ ፡ ሁሉ ፡ ምንድ
ነው ፡ አትበል ።
፲፰ እነሆ ፡ ይህ ፡ ሰማይ ፡ ከሰማይም ፡ በላይ ፡ ያለ ፡
ሰማይ ፡ ከሰማይም ፡ በታች ፡ ያለ ፡ ውቅያኖስ ፡
ምድርም ፡ በመዓት ፡ በጐበኛቸው ፡ ጊዜ ፡ ይህ ፡
ሁሉ ፡ ያልፋል ።
፲፱ ተራሮችም ፡ የምድርም ፡ መሠረት ፡ በመዓት ፡
ባየቸው ፡ ጊዜ ፡ ይንቀጠቀጣሉ ፡ ይነዋወጣሉ ።
፳ ይህንንም ፡ ልብ ፡ አያስበውም ፡ የእግዚአብሔ
ርን ፡ ሥራውን ፡ ማን ፡ ያውቃል ፡ ገናንነቱንስ ፡
ጠንቅቆ ፡ ማን ፡ ያውቃል ።
፳፩ ሰው ፡ የማያየው ፡ ፍጥረቱ ፡ ነፋስ ፡ ነው ፡ ከሰው ፡
የተሠወረ ፡ ፍጥረቱም ፡ ብዙ ፡ ነው ።
፳፪ እውነት ፡ ሥራ ፡ መሥራትን ፡ ማን ፡ ያስተም
ራል ፡ የይቅርታውንስ ፡ አለኝታ ፡ ማን ፡ ደጅ ፡
ይጠናል ።
፳፫ አእምሮ ፡ የሌለው ፡ ሰው ፡ እንዲህ ፡ ያስባል ፡
ሰነፍ ፡ በደለኛ ፡ ሰውም ፡ ስንፍናን ፡ ያስባል ።
፳፬ ልጄ ፡ ስማኝ ፡ ጥበብንም ፡ ተማር ፡ ነገሬንም ፡
ከልቡናህ ፡ አድምጠው ።
፳፭ በልቡናህ ፡ መርምረህ ፡ ጥበብህን ፡ ግለጣት ፡
የትምህርትህንም ፡ ምሥጢሯን ፡ ተረዳ ።
፳፮ የእግዚአብሔር ፡ ፍጥረቱ ፡ ለይኩን ፡ በለው ፡
ቃሉ ፡ ተፈጠረ ፡ በየወገናቸውም ፡ ሥራታቸ
ውን ፡ ለየ ።
፳፯ ይህ ፡ ዓለም ፡ ጸንቶ ፡ በሚኖር ፡ ግንዘብ ፡ ሥራ
ውን ፡ ሁሉ ፡ አዘጋጀ ፡ ሠራዊታቸውንም ፡ በየ
ወገናቸው ፡ አዘጋጀ ፡ ይኸንን ፡ የፈጠራቸው ፡
እግዚአብሔር ፡ አይራብም ፡ አይጠማም ። ብር
ሃናቸውም ፡ አይፈጸምም ።
፳፰ አንዱ ፡ ካንዱ ፡ ጋራ ፡ አይጨናነቅም ፡ ለዘለዓ
ለሙ ፡ ከቃሉ ፡ አይወጡም ።
፳፱ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይህን ፡ ዓለም ፡
ጎበኘ ፡ ዝናምንም ፡ አጠገበ ።
፴ በደማዊት ፡ ነፍስ ፡ ሕያው ፡ የሆነ ፡ ፍጥረት ፡
ሁሉ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ መላ ፡ መመለሻቸውም ፡
ወደ ፡ መቃብር ፡ ነው ።

ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

፩ እግዚአብሔር ፡ አዳምን ፡ ከምድር ፡ ፈጠ
ረው ፡ዳግመኛም ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ይመልሰዋል።
፪ ዘመንን ፡ ቀንን ፡ በቍጥር ፡ ሰጣቸው ፡ በውስ
ጧም ፡ ያለውን ፡ ፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ አስገዛቸው ።
እየራሳቸው ፡ ኃይልን ፡ አሳደረባቸው ፡ በምሳሌ ፫
ውም ፡ ፈጠራቸው ።
ፍጥረቱ ፡ ሁሉ ፡ ይፈሩዋቸው ፡ ዘንድ ፡ እንዲፈ ፬
ሩዋቸው ፡ አደረገ ።
ከብቶችንና ፡ አውሬዎችን ፡ ወፎችንም ፡ ይገዟ ፭
ቸው ፡ ዘንድ ፡ እንዲገዟቸው ፡ አደረገ ።
አንደበትንና ፡ ቃልን ፡ ጆሮንና ፡ ዓይንን ፡ በሚ ፮
ያስቡ ፡ ገንዘብ ፡ ልቡናንም ፡ ሰጣቸው ።
ጥበብን ፡ ማወቅንም ፡ አጠገባቸው ፡ ክፉንና ፡ ፯
በጎንም ፡ አሳያቸው ።
የሥራውን ፡ ገናንነት ፡ መፈራቱንም ፡ ያሳያ ፰
ቸው ፡ ዘንድ ፡ በልቡናቸው ፡ ፍርሃትን ፡ አሳደ
ረባቸው ።
የከበረ ፡ ስሙን ፡ ያመሰግኑት ፡ ዘንድ ። ፱
የሥራውንም ፡ ገናንነት ፡ ይናገሩ ፡ ዘንድ ፡ ፍር ፲
ሃትን ፡ አሳደረባቸው ።
ጥበብን ፡ ሰጣቸው ፡ የሚያድናቸው ፡ ሕጉንም ፡ ፲፩
አወረሳቸው ።
ለዘለዓለም ፡ ጸንቶ ፡ የሚኖር ፡ መሐላንም ፡ ተማ ፲፪
ማላቸው ፡ ፍርዱንም ፡ ነገራቸው ።
የጌትነቱንም ፡ ገናንነት ፡ ዓይኖቻቸው ፡ አዩ ። ፲፫
ከኃጢአቱ ፡ ሁሉ ፡ ተጠበቁ ፡ አላቸው ። ፲፬
የጌትነቱንም ፡ ቃል ፡ ጆሮቻቸው ፡ ሰሙ ፡ ሁሉ ፲፭
ንም ፡ ባልንጀራችሁን ፡ ውደዱ ፡ ብሎ ፡ አዘዛ
ቸው ።
ሥራቸውም ፡ ሁለጊዜ ፡ በፊቱ ፡ ነው ፡ ከይኖ ፲፮
ቹም ፡ የሚሠወሩበት ፡ የላቸውም ።
ለአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ነገሥታቱን ፡ አነገሠላቸው ። ፲፯
እስራኤል ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔር ፡ እድል ፡ ሆነ ። ፲፰
ሥራቸውም ፡ ሁሉ ፡ በፊቱ ፡ እንደ ፡ ፀሐይ ፡ ፲፱
ነው ፡ ዓይኖቹም ፡ ሁለጊዜ ፡ ሥራቸውን ፡ ያያሉ ።
ኃጢአታቸውም ፡ ከሱ ፡ አልተሠወረችም ፡ በደ ፳
ላቸውም ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ የተገ
ለጠ ፡ ነው ።
የሰው ፡ ምጽዋቱ ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ እንደ ፡ ማኅ ፳፩
ተም ፡ ነው ።
የሰው ፡ ዋጋው ፡ እንደ ፡ ዓይን ፡ ብሌኑ ፡ ትጠበ ፳፪
ቃለታለች ።
ኋላ ፡ ተመልሶ ፡ ዋጋቸውን ፡ ይሰጣቸዋል ፡ የኃ ፳፫
ጢአታቸውንም ፡ ፍዳ ፡ ወደ ፡ ራሳቸው ፡ ይመ
ልሳል ።
ነገር ፡ ግን ፡ ንስሐ ፡ የሚገቡትን ፡ ምክንያት ፡ ፳፬
ሰጣቸው ፡ ተስፋቸውን ፡ ያጡ ፡ ሰዎችንም ፡
ደስ ፡ ያሰኛቸዋል ።
በንስሐ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተመለስ ፡ ኃጢ ፳፭
አትንም ፡ ተዋት ፡ ከኃጢአትህ ፡ ተመልሰህ ፡
በፊቱ ፡ ተለማመጥ ።
ፈጽመህ ፡ ከኃጢአትህ ፡ በንስሐ ፡ ወደ ፡ እግዚ ፳፮
አብሔር ፡ ተመለስ ፡ ኃጢአትን ፡ ሁሉ ፡ ጥላ ፡
የእግዚአብሔርንም ፡ ፈቃድ ፡ ፈጽም ።
በሕይወት ፡ ሳሉ ፡ እንደሚገዙለት ፡ ሰዎች ፡ ፳፯
እግዚአብሔርን ፡ በመቃብር ፡ የሚያመሰግነው ፡
ማነው ።

፳፰፤ የሞተ ፡ ሰውን ፡ ግን ፡ ንስሐ ፡ እንደ ፡ ኢ.ምንት ፡
አለፈው ፡ በሕይወት ፡ ሳለህ ፡ ደስ ፡ እያለህ ፡ እግ
ዚአብሔርን ፡ አመስግነው ።
፳፱፤ የእግዚአብሔር ፡ ቸርነቱ ፡ ብዙ ፡ ነውና ፡ የሚ
ገዙለትን ፡ ሰዎች ፡ ይቅር ፡ ይላቸዋል ።
፴፤ ሰው ፡ ሟች ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በሕይ
ወት ፡ ጸንቶ ፡ መኖርን ፡ አይችልምና ፡ ይቅር ፡
ይላቸዋል ።
፴፩፤ ከፀሐይ ፡ የሚነጻ ፡ ምን ፡ አለ ፡ እሱስ ፡ ስንኳ ፡
ያልፋል ። እንዲህ ፡ መሆን ፡ ሳለ ፡ ደማዊና ፡
ሥጋዊ ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡ ያስባል ።
፴፪፤ እሱ ፡ ግን ፡ የሰማይን ፡ ምጥቀት ፡ ያውቃል ፡
ሰው ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ አመድ ፡ ትቢያ ፡ ነው ።

ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

፩፤ ለዘለዓለም ፡ በሕያውነት ፡ የሚኖር ፡ እሱ ፡
እግዚአብሔር ፡ ሁሉን ፡ አንድነት ፡ ፈጠረ ።
፪፤ እውነተኛ ፡ እግዚአብሔር ፡ ብቻ ፡ ነው ።
፫፤ ሥራውን ፡ ያውቅ ፡ ዘንድ ፡ ማንም ፡ ማን ፡ አላ
ሰናበተውም ፡ ገናንነቱንስ ፡ ማን ፡ መርምሮ ፡
ያውቃል ።
፬፤ ከሀሊነቱንስ ፡ ማን ፡ መርምሮ ፡ አወቀው ፡ ቸር
ነቱንስ ፡ ማን ፡ ጠንቅቆ ፡ ይናገራል ።
፭፤ ሥነ ፡ ፍጥረት ፡ አነሰ ፡ ብሎ ፡ መጨመር ፡ በዛ ፡
ብሎም ፡ መክፈል ፡ አይገባም ፡ የእግዚአብ
ሔርን ፡ ጌትነቱን ፡ መርምሮ ፡ የሚያገኘው ፡
የለም ።
፮፤ በፈጠረው ፡ ጊዜ ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ ሰውን ፡ ያዘዋል ፡
ዘመኑንም ፡ በስጨረሰው ፡ ጊዜ ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡
በሞት ፡ ያሳርፈዋል ።
፯፤ ሰው ፡ ምን ፡ ቁም ፡ ነገር ፡ ነው ፡ ጥቅሙስ ፡
ምንድነው ።
፰፤ መቶ ፡ ዘመን ፡ የሚሆን ፡ የዘመኑ ፡ ቍጥር ፡ በባ
ሕሩ ፡ ውኃ ፡ ሁሉ ፡ እንዳለች ።
፱፤ እንደ ፡ አንዲት ፡ ውኃ ፡ ጠብታ ፡ ከሻዋውም ፡
ሁሉ ፡ እንደ ፡ አንዲት ፡ አሸዋ ፡ ቅንጣት ፡ የሚ
ሆን ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ከሚመላለሰው ፡ ዘመን ፡
ሁሉ ፡ ዘመኑ ፡ ጥቂት ፡ የሚሆን ፡ የሰው ፡ በጎነ
ቱስ ፡ ክፋቱስ ፡ ምንድነው ።
፲፤ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ እግዚአብሔር ፡ ይታገሣቸዋል ።
፲፩፤ አሁን ፡ እንደ ፡ ተናገርሁት ፡ ቸርነቱን ፡ አብዝቷ
ልና ፡ ፍጻሜ ፡ ዘመናቸው ፡ ክፉ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
አይቶ ፡ አውቆ ፡ ቸርነቱን ፡ አሳደረባቸው ።
፲፪፤ ሰው ፡ ባልንጀራውን ፡ ብቻ ፡ ይቅር ፡ ይላል ፡
እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ፍጥረቱን ፡ ሁሉ ፡ ይቅር ፡
ይላል ፡ ይቆጣል ፡ በመከራ ፡ ይገርፋል ፡ ይቅር ፡
ይላል ፡ እረኛ ፡ መንጋውን ፡ እንዲመልስ ፡ በን
ስሐ ፡ ይመልሳል ።
፲፫፤ በተግሣጹ ፡ የሚታገሡትን ፡ ሕጉንም ፡ የሚጠ
ብቁትን ፡ ሰዎች ፡ ይቅር ፡ ይላቸዋል ።
፲፬፤ ልጄ ፡ በምጽዋትህ ፡ መካከል ፡ ኃዘንን ፡ አታ
ግባ ፡ በምትሰጠውም ፡ ሁሉ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አት
ናገር ።
፲፭፤ ዝናም ፡ ዋዕይን ፡ እንዲያቀዘቅዘው ፡ እንደዚሁ ፡
ክፉ ፡ ነገር ፡ ተናግሮ ፡ ከመስጠት ፡ በጎ ፡ ነገር ፡
ተናግሮ ፡ መንሣት ፡ ይሻላልና ፡ በምትሰጠው ፡
ሁሉ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አትናገር ። ነገር ፡ ግን ፡ ሁለ
ቱም ፡ ሁሉ ፡ በደግ ፡ ሰው ፡ ዘንድ ፡ ይገኛሉ ።
ንፉግ ፡ ሰው ፡ ልቡናውን ፡ ቅር ፡ እያለው ፡ ይሰ ፲፮፤
ጣል ።
ሰነፍም ፡ ይሰገዳል ፡ አያመሰግንም ። ፲፯፤
ሳትናገር ፡ አስቀድመህ ፡ ነገሩን ፡ ተረዳ ፡ በኃጢ ፲፰፤
አት ፡ ሳትታመም ፡ ንስሐ ፡ ግባ ።
ሳይፈረድብህ ፡ ተዋረድ ፡ በመከራህም ፡ ጊዜ ፡ ፲፱፤
ይቅርታ ፡ ታገኛለህ ።
ሳትደክም ፡ ራስህን ፡ እዋርድ ፡ በበደልህም ፡ ፳፤
ጊዜ ፡ ተለማመጥ ።
ስእለትህን ፡ አታስቀር ፡ ፈጥነህ ፡ ስጥ ፡ ሳትሞ ፳፩፤
ትም ፡ ጽድቅን ፡ ሥራት ።
ሳትሳልም ፡ አስቀድመህ ፡ ስእለትህን ፡ አዘጋጅ ፡ ፳፪፤
እግዚአብሔርን ፡ እንደሚፈታተነው ፡ ሰው ፡
አትሁን ።
በተቈጣህም ፡ ጊዜ ፡ የምትሞትበትን ፡ ቀን ፡ ፳፫፤
አስባት ፡ ፍዳ ፡ የምትቀበልበትን ፡ ቀን ፡ አስበህ ፡
ንስሐ ፡ ገብተህ ፡ ተለማመጥ ።
በጠገብህበትም ፡ ወራት ፡ የተራብህበትን ፡ ፳፬፤
ወራት ፡ አስብ ።
እነዋወር ፡ ከጧት ፡ እስከ ፡ ማታ ፡ ድረስ ፡ ትለ ፳፭፤
ዋወጣለችና ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ዘንድ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ፈጥኖ ፡ ይደረጋልና ፡ በተ
ሾምህበትም ፡ ወራት ፡ የተሻርህበትን ፡ ወራት ፡
አስብ ።
አዋቂ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ፈርቶ ፡ በሁሉ ፡ ይጠበቃል ፡ ፳፮፤
በበደልህበት ፡ ወራት ፡ ንስሐ ፡ ግባ ።
አዋቂ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ጥበብን ፡ ያገኛታል ፡ ያገ ፳፯፤
ኛትንም ፡ ሰው ፡ ታሰምነዋለች ፡ ታስፈራዋለች ።
እነዚያ ፡ ነገር ፡ አዋቂዎች ፡ በልቡናቸው ፡ ይራ ፳፰፤
ቀቃሉ ፡ የተረዳ ፡ ምሳሌንም ፡ ይናገራሉ ።
ሄደህ ፡ የኃጢአትን ፡ ፈቃድ ፡ አትከተል ፡ ከክ ፳፱፤
ፉም ፡ ፈቃድ ፡ ራቅ ።
ለሰውነትህ ፡ የወደደችውንስ ፡ ከሰጠኻት ፡ ፴፤
ጠላትህን ፡ ባንተ ፡ የጨከነ ፡ ታደርገዋለች ።
ከብ ፡ ደስ ፡ ይልህ ፡ ዘንድ ፡ በኃጢአት ፡ ሳለህ ፡ ፴፩፤
ባለጸግነትን ፡ አትለምን ።
በፍዳ ፡ እንዳትያዝ ፡ አንተ ፡ ድሀ ፡ ሆነህ ፡ ሳለህ ፡ ፴፪፤
በቀማዳህም ፡ ምንም ፡ ምን ፡ ሳይኖርህ ፡ አትበ
ደር ።

ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

እንጥረኛ ፡ መሸተኛ ፡ አይከብርም ፡ ጥቂት ፡ ፩፤
ገንዘብ ፡ የሚያቃልል ፡ ሰው ፡ ብዙ ፡ ገንዘብን ፡
ያጠፋል ።
ሴቶችና ፡ መጠጥ ፡ መምህራንን ፡ ያስቷቸዋል ፡ ፪፤
ጋለሞታን ፡ የሚከተላት ፡ ሰው ፡ በደለኛ ፡ ነው ።
የዚህ ፡ ሰው ፡ ፍጻሜው ፡ ትሉ ፡ የማያንቀላፋ ፡ ፫፤
እሳቱ ፡ የማይጠፋ ፡ ነው ፡ ደፋር ፡ ሰውነት ፡ ከመ
ከራ ፡ አትጠበቅም ።
ፈጥኖ ፡ የሚያምን ፡ ሰው ፡ ልቡናው ፡ ቀሊል ፡ ፬፤

ነው ፡ ኃጢአት ፡ የሚሠራ ፡ ሰውም ፡ ሰውነቱን ፡
ይበድላል ።
፭ ልቡናውን ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ሰው ፡ ይደነቃል ።
፮ ብዙ ፡ መናገርን ፡ የሚጠላ ፡ ሰው ፡ ኃጢአቱን ፡
ይከፍላታል ።
፯ የሰማኸውን ፡ ቃል ፡ አታውጣ ፡ ለዘላለሙ ፡ እን
ዳሰብህ ፡ አትድገም ።
፰ በጠላትህና ፡ በወዳጅህ ፡ ዘንድ ፡ የምትናገረው ፡
ነገር ፡ አይኑር ፡ ስተህ ፡ የሠራኸው ፡ ኃጢአት
ህንም ፡ አትናገር ።
፱ ከሰማ ፡ በኋላ ፡ ኃጢአትህን ፡ አይሠውርልህ
ምና ፡ እስክትሞትም ፡ ድረስ ፡ ይጠብቅሃልና ፡
ስተህ ፡ የሠራኸውን ፡ ኃጢአትህን ፡ አትናገር ።
፲ የሰማኸውን ፡ ቃል ፡ አታውጣ ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡
የሚያገኝህ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ እንደሌለ ፡ እወቅ ።
፲፩ ቀሊል ፡ ሰው ። የሰማውን ፡ ነገር ፡ እስኪያወጣ ፡
ድረስ ፡ እአምሮውን ፡ ያጣል ፡ ልጅ ፡ የምትወ
ልድ ፡ ሴት ፡ በምጥ ፡ እንድትጨነቅ ፡ እንደዚ
ያች ፡ ይጨነቃል ።
፲፪ የተወጋም ፡ ሰው ፡ ጦሩን ፡ ከላዩ ፡ ይነቅል ፡ ዘንድ ፡
እንዲቻኩል ፡ ቀሊል ፡ ሰውም ፡ የሰማውን ፡
ቃል ፡ ያወጣ ፡ ዘንድ ፡ እንደዚያ ፡ ይቻኩላል ።
፲፫ ወዳጅህን ፡ ተቈጣው ፡ ወይ ፡ አላደረገም ፡ ይሆ
ናል ፡ ቢያደርግም ፡ እንዳይደግም ፡ ተቈጣው ።
፲፬ ወዳጅህን ፡ ተቈጣው ፡ ወይ ፡ አልተናገረም ፡ ይሆ
ናል ፡ ቢናገርም ፡ እንዳይደግም ፡ ተቈጣው ።
፲፭ ወዳጅህን ፡ ተቈጣው ፡ ወይ ፡ በጥል ፡ በቃ ፡ አጣ
ልተውት ፡ ይሆናል ፡ በልቡናው ፡ ሳይወድ ፡
የሚስት ፡ ሰው ፡ አለና ፡ የነገሩህን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡
አትስማ ።
፲፮ ባንደበቱ ፡ ያልሳተ ፡ ሰው ፡ የተደነቀ ፡ ነው ።
፲፯ ቍጣ ፡ ሳይበዛ ፡ ወዳጅህን ፡ ተቈጣው ፡ ጥበብ ፡
ሁሉ ፡ ሕጉን ፡ የምታሠራ ፡ ስለ ፡ ሆነች ፡ ጥበብ ፡
ሁሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ ነውና ።
፲፰ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ ብለህ ፡ የጸናች ፡
ቍጣን ፡ አሳልፋት ፡ ጥበብ ፡ ሁሉ ፡ ሕጉን ፡ ታስ
ጠብቀዋለችና ። ጥበብ ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡
መፍራት ፡ ነው ።
፲፱ ክፉ ፡ ነገርን ፡ የሚያስተምር ፡ ጥበብ ፡ የለም ።
ለኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ ምክር ፡ ጥበብ ፡ የላትም ።
፳ ከሁሉ ፡ የምትረክስ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አለች ፡ አእ
ምሮ ፡ የሌለው ፡ ነፍስ ፡ አለ ።
፳፩ ነገር ፡ ግን ፡ ስትራቀቅ ፡ የእግዚአብሔርንም ፡
ሕግ ፡ ስታፈርስ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈራው ፡
ሰነፍ ፡ ሰው ፡ ይሻላል ።
፳፪ እየበደለ ፡ የሚራቀቅ ፡ የሚጠነቀቅ ፡ ሰው ፡ አለ ፡
ለባልንጀራው ፡ የሚያደላ ፡ ለወዳጁም ፡ ፍር
ዱን ፡ የሚያቀና ፡ መስሎ ፡ ፍርድን ፡ የሚለው
ጣት ፡ ሰው ፡ አለ ።
፳፫ ሳያመሰግነው ፡ ለክፉ ፡ ነገር ፡ የሚያደላ ፡ ሰው ፡
አለ ። ልቡናው ፡ ግን ፡ ክደትን ፡ መልቷል ።
፳፬ በልቡናው ፡ ሌላ ፡ ነገር ፡ ሳለ ፡ ፊት ፡ አይቶ ፡
የሚያደላ ፡ አለ ፡ ያላሰብከውም ፡ መከራ ፡ ይመ
ጣብሃል ።

ኃይሉ ፡ ቢደክም ፡ ባንትም ፡ ክፉ ፡ ማድረግ ፡ ፳፭
ቢሳነው ፡ ያስትህ ፡ ዘንድ ፡ የሚያስፈራ ፡ ሥራን ፡
ያመጣብሃል ፡ ያሳዝንሃል ።
ሰው ፡ በመልኩ ፡ ይታወቃልና ፡ የብልህ ፡ ሰው ፡ ፳፮
ጥበቡ ፡ በፊቱ ፡ ይታወቃል ።
ከአባበሱ ፡ ከረማመዱ ፡ ከከሂዱ ፡ ከሣቁም ፡ የተ ፳፯
ነሣ ፡ የሰው ፡ ሥራው ፡ ይታወቃል ።

ምዕራፍ ፡ ፳ ።

ለበጎ ፡ ነገር ፡ ሳይሆን ፡ የሚቈጣ ፡ ሰው ፡ አለ ፡ ፩
አዋቂ ፡ ሆኖ ፡ ሳለ ፡ ዝም ፡ የሚል ፡ ሰው ፡ አለ ።
ነገር ፡ ግን ፡ ሳትነቅፍ ፡ ብትቈጣ ፡ ይሻላል ። ፪
በኃጢአቱ ፡ ጸንቶ ፡ መኖር ፡ ተስኖታልና ። ፫
ንስሐ ፡ ገብቶ ፡ የሚለማመጥ ፡ ሰው ፡ አለ ።
ሻንደረብ ፡ ፈቃዱ ፡ ሳይፈጽምለት ፡ ቆንጆ ፡ ፬
ልጅን ፡ እንዲወድ ፡ እንደዚሁ ፡ ፍርድን ፡ ያደላ ፡
ዘንድ ፡ የሚወድ ፡ ሰው ፡ አለ ።
እያወቀ ፡ ዝም ፡ የሚል ፡ ሰው ፡ አለ ፡ ብዙ ፡ ነገር ፡ ፭
ከመናገሩ ፡ የተነሣ ፡ ራሱን ፡ የሚያስጠላ ፡ ሰው ፡
አለ ።
የሚመልሰውን ፡ አያውቅምና ፡ ዝም ፡ የሚል ፡ ፮
ሰው ፡ አለ ፡ ጊዜውንም ፡ እስኪያገኝ ፡ ድረስ ፡
ዝም ፡ የሚል ፡ ሰው ፡ አለ ።
አዋቂ ፡ ሰው ፡ ጊዜውን ፡ እስኪያገኝ ፡ ድረስ ፡ ፯
ዝም ፡ ይላል ፡ ሰነፍ ፡ ደፋር ፡ ሰው ፡ ግን ፡ እንዳ
ገኘ ፡ ይናገራል ።
ነገርን ፡ የሚያበዛን ፡ ሰው ፡ ይቈጡታል ፡ ራሱ ፡ ፰
ንም ፡ የሚያከራ ፡ ሰውን ፡ ይጠሉታል ።
መከራው ፡ የሚያዋርደው ፡ ሰው ፡ አለ ፡ ገንዘብ ፡ ፱
አግኝቶም ፡ የማይኖርለት ፡ ሰው ፡ አለ ።
የማይጠቅምህን ፡ ገንዘብ ፡ የሚሰጥህ ፡ ሰው ፡ ፲
አለ ። እጥፍ ፡ አድርጎ ፡ ይቀበልህም ፡ ዘንድ ፡
የሚሰጥህ ፡ ሰው ፡ አለ ።
እየተቸገረ ፡ ራሱን ፡ የሚያከራ ፡ ሰው ፡ አለ ፡ ፲፩
ክብሮ ፡ ሳለ ፡ ራሱን ፡ የሚያዋርድ ፡ ሰው ፡ አለ ።
በጥቂት ፡ ገንዘብ ፡ ብዙ ፡ ገንዘብ ፡ የሚገዛ ፡ አለ ፡ ፲፪
ሰባት ፡ እጥፍ ፡ ያደርገውም ፡ ዘንድ ፡ ይፈልጋል ።
በቃሉ ፡ አዋቂ ፡ የሆነ ፡ ራሱን ፡ ወደ ፡ መኳን ፲፫
ንት ፡ ያስጠጋል ፡ ለሰነፎች ፡ ስጦታ ፡ መወደድ ፡
የላትም ።
ሰነፍ ፡ ሰው ፡ መወደድና ፡ ጥቅም ፡ የሌለውን ፡ ፲፬
ገንዘብ ፡ ይሰጥሃል ፡ ጥቂት ፡ ገንዘብም ፡ ቢሰጥህ ፡
ለልቡ ፡ ብዙ ፡ ገንዘብ ፡ የሰጠህ ፡ ይመስለዋል ።
ጥቂት ፡ ገንዘብም ፡ ቢሰጥህ ፡ ብዙ ፡ ገንዘብ ፡ ፲፭
እንደ ፡ ሰጠህ ፡ ያደርገዋል ፡ ይለገድብሃል ፡ ባንታ ፡
አንደበቱን ፡ ከፍ ፡ ዝቅ ፡ አድርጎ ፡ ይናገርሃል ፡
የሰጠህን ፡ ይናገርብህ ፡ ዘንድ ፡ አደባባይ ፡ ላይ ፡
ይዘራል ፡ ዛሬ ፡ ቢሰጥህ ፡ ነገ ፡ ይከፈልሃል ፡ እን
ዲህ ፡ ያለው ፡ ሰው ፡ ለሰው ፡ የሚያስጠላ ፡ ነው ።
በጎ ፡ ነገር ፡ ያደረግሁለት ፡ እኔ ፡ ዋጋን ፡ አላገኘ ፲፮
ምና ፡ ሰነፍ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ወዳጅ ፡ አልፈልግም ፡
ምን ፡ ይጠቅመኛል ፡ ይላል ፡ እሊህንም ፡ የሚ
መገቡ ፡ ሰዎች ፡ በኔ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ይናገራሉ ፡
አለ ።

፲፯፤ ሁሉም፡ሁለጊዜ፡ያሙኛል፡በኔም፡ይስቃሉ።
፲፰፤ በንደበትህ፡ከትሰንከከል፡በምድር፡ላይ፡ብት
ወድቅ፡ይሻልሃል፡እንደዚሁ፡ሁሉ፡የጾናች፡
መከራ፡ፈጥና፡ትመጣለች።
፲፱፤ እንዳገኘ፡የሚናገር፡ሰው፡ራሱን፡ያስጠላል፡
ለቃሉም፡መወደድ፡የለውም፡በሰነፎችም፡
አንደበት፡ነገር፡ይጠላል።
፳፤ በጊዜዋ፡ጊዜ፡አይናገራትምና፡በሰነፍ፡ሰው፡
አንደበት፡መስሎ፡የሚናገረው፡ነገር፡ይጠ
ላል።
፳፩፤ በተቸገረ፡ጊዜ፡እግዚአብሔርን፡ወደ፡መፍ
ራት፡የሚመለስ፡ሰው፡አለ፡ሰውነቱም፡በተ
ድላ፡በደስታ፡ታርፋለች።
፳፪፤ ሰውን፡አፍሮ፡ሰውነቱን፡የሚያጠፋ፡አለ፡
በስንፍናውም፡ሰውነቱን፡ያጠፋል።
፳፫፤ ሰውን፡አፍሮ፡ሳይሰጠው፡ለወዳጁ፡ተስፋ፡
የሚሰጠው፡አለ። ስለዚህ፡ነገር፡በከንቱ፡
ጠላት፡ይሆነዋል።
፳፬፤ የሐሰተኛ፡ሰው፡ጉስቊልናው፡ጽኑ፡ነው፡
የሰነፎችም፡ነገራቸው፡የተጠላ፡ነው።
፳፭፤ አሰት፡ከመናገር፡መስረቅ፡ይሻላል፡አሰተኛ፡
ሰው፡ይጐሰቊላል፡ፈጽሞም፡ያፍራልና።
፳፮፤ ነገር፡ግን፡የሁለቱም፡ሁሉ፡ፍጻሜያቸው፡
ሞት፡ውርደት፡ነው።
፳፯፤ በቃሉ፡አዋቂ፡የሆነ፡ሰው፡ነገሩ፡ይሰማል፡
ብልህ፡ሰው፡መኳንንቱን፡ያገለግላል።
፳፰፤ ምድርን፡የሚያርሳት፡የሚቈፍራት፡ሰው፡
የእህሉን፡ክምር፡ያበዛል፡መኳንንቱንም፡
የሚያገለግል፡ሰው፡ራሱን፡ይጠቅማል።
፳፱፤ እጅ፡መንሻ፡መማለጃ፡አዋቆች፡ሰዎችን፡
ዓይነ፡ልቡናቸውን፡ይሠውራቸዋል፡አፉቸ
ውን፡ይዘጋዋል፡ቃላቸውንም፡ያስለውጣቸ
ዋል።
፴፤ የተሠወረ፡ጥበብ፡እንደ፡ተቀበረ፡ወርቅ፡
ነው፡የሁለቱስ፡ጥቅማቸው፡ምንድነው።
፴፩፤ ጥበቡን፡ከሚሠውር፡ከዋቂ፡ሰው፡ስንፍና
ውን፡የሚሠውር፡ሰነፍ፡ሰው፡ይሻላል።

ምዕራፍ፡፳፩።

፩፤ ልጄ፡የበደልከው፡በደል፡የሳትከው፡ነገር፡
እንዳለ፡እወቅ፡ከዚህ፡በኋላ፡ዳግመኛ፡አት
በድል፡ስለ፡ቀደመውም፡ኃጢአትህ፡ንስሐ፡
ግባተህ፡ተለማመጥ።
፪፤ ሰው፡ከክፉ፡አውሬ፡እንዲሸሽ፡እንደሱ፡
ከኃጢአት፡ሽሽ፡ደስ፡ካሰኘችህስ፡ከፍዳ፡
አታወጣህም፡ጥርሷ፡እንደ፡አንበሳ፡ጥርስ፡
ነው፡የሰውን፡ሰውነት፡ታጠፋለች።
፫፤ በሁለት፡ወገን፡ስለት፡ያለው፡ሰይፍ፡እንዲ
ያጠፋ፡ኃጢአት፡ሁሉ፡እንደዚሁ፡ያጠፋል፡
ከቈሰለችም፡ዘንድ፡ለቍስሏ፡ድኅነት፡የለ
ውም።
፬፤ መመከትና፡መታበይ፡ትዕቢትም፡ባለጸግነ
ትን፡ያጠፉታል፡እንደዚሁም፡ሁሉ፡የትዕ
ቢተኞችን፡ቤት፡ያጠፋሉ።
ድሀ፡በለመነ፡ጊዜ፡አፉን፡እስከ፡ገሮሮው፡ ፭፤
ድረስ፡ይከፍታል፡ጩኸቱም፡ፈጥኖ፡ወደ፡
እግዚአብሔር፡ይደርሳል።
ምክርን፡የሚጠላ፡ሰው፡ኃጢአተኞችን፡ ፮፤
ይመስላቸዋል። እግዚአብሔርን፡የሚፈራ፡
ሰው፡ግን፡በመከራት፡ጊዜ፡ልቡናውን፡
ከኃጢአት፡ይመልሳል።
ነገር፡የሚችል፡ሰው፡ከሩቅ፡ይታወቃል፡ ፯፤
አዋቂ፡ሰውን፡ግን፡የተሳተው፡ኃጢአቱ፡
ይታወቀዋል።
እየተበደረ፡ቤቱን፡የሚሠራ፡ሰው፡ሥራው፡ ፰፤
እንደ፡ክረምት፡ሥራ፡ነው።
የኃጢአተኞችም፡ወገናቸው፡እንደ፡ገለባ፡ ፱፤
ክምር፡ነው፡ፍጻሜያቸውም፡ለገሃነም፡ይሆ
ናል።
የኃጢአተኞች፡ሥራቸው፡ክፉ፡ነው፡ፍጻ ፲፤
ሜዋም፡ገሃነም፡ነው።
ልቡናውን፡ያጸና፡ሰው፡የእግዚአብሔርን፡ ፲፩፤
ሕግ፡ይጠብቃል። እግዚአብሔርን፡የመፍ
ራት፡መጨረሻ፡ጥበብ፡ነው።
ያልተማረ፡ሰው፡አይራቀቅም፡የሚማርም፡ ፲፪፤
ሰው፡አለ። በጉስቊልናው፡ላይ፡ጉስቊልና፡
ይጨመርለታል።
የብልህ፡ሰው፡አሳቡ፡እንደ፡ክረምት፡ውኃ፡ ፲፫፤
ነው፡ምክሩም፡እንደ፡ገነት፡ውኃ፡ብዙ፡
ነው።
የሰማውን፡ነገር፡ሁሉ፡ማስቀረት፡አይችል ፲፬፤
ምና፡የቀሊል፡ሰው፡ልቡና፡እንደ፡ሰባራ፡
ማድጋ፡ነው።
አዋቂ፡ሰው፡የጥበብን፡ነገር፡በሰማ፡ጊዜ፡ ፲፭፤
ያደንቂታል፡ዳግመኛም፡በጥበብ፡ላይ፡ጥበ
ብን፡ይጨምራል። ክፉ፡ልቡና፡ግን፡ከሰማ፡
በኋላ፡ይሃድፋል፡ወደ፡ኋላም፡ይመልሰዋል።
የሰነፍ፡ሰው፡ነገሩ፡በሩቀ፡ጐዳና፡እንዳለ፡ ፲፮፤
እንደሚከብድ፡ሸክም፡ነው፡ያዋቂ፡ሰው፡
አንደበት፡መወደድ፡ግን፡ያማረ፡ነው።
የአዋቂ፡ሰው፡ነገሩ፡በደባበይ፡ይሰማል፡ነገ ፲፯፤
ሩም፡ወደ፡ሰው፡ልቡና፡ይገባል።
በሰነፎች፡ሰዎች፡ዘንድ፡ጥበብ፡እንደ፡ፈረ ፲፰፤
ሰች፡ቤት፡ናት። የሰነፍ፡ሰው፡ምክርም፡
የማይወደድ፡ነገር፡ነው።
የሰነፎች፡ትምህርት፡እንደ፡ታሠረ፡እግር፡ ፲፱፤
ነው። የሰነፎች፡ልቡና፡ቀኝ፡እጁን፡እንደ፡
ታሠረ፡ሰው፡ደካማ፡ነው።
ሰነፍ፡ሰው፡በሳቀ፡ጊዜ፡ቃሉን፡ከፍ፡ከፍ፡ ፳፤
ያደርጋል፡ብልህ፡ሰው፡ግን፡በጭንቅ፡ከን
ፈሩን፡ፍግግ፡ያደርጋል።
በዋቂ፡ሰው፡ዘንድ፡ጥበብ፡እንደ፡ወርቅ፡ ፳፩፤
ጌጥ፡ነው፡በቀኝ፡እጅ፡እንዳለ፡ማልደያም፡
ነው።
የሰነፍ፡ሰው፡እግሩ፡ፈጥና፡ወደ፡ቤት፡ትገ ፳፪፤
ባለች፡በትምህርት፡የተነከ፡ሰው፡ግን፡የሰው፡
ፊት፡ያፍራል።
ሰነፍ፡ሰው፡በደጃፍ፡ቆሞ፡የሰው፡ቤት፡ይጎ ፳፫፤

በኛል ፡ አዋቂ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ በውጭ ፡ ይቆማል ።
፳፬፤ የሰው ፡ ስንፍናው ፡ በውጭ ፡ ትሰማለች ፡ በዋቂ ፡
ሰው ፡ ዘንድ ፡ ግን ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ማድስል ፡
ጭንቅ ፡ ነው ።
፳፭፤ ከብልሁ ፡ በተለየ ፡ በሰነፉ ፡ ዘንድ ፡ ይህ ፡ ነገር ፡
ጭንቅ ፡ ነው ፡ መምህራን ፡ ነገራቸውን ፡ መጥ
ነው ፡ ይናገሩታል ።
፳፮፤ የሰነፎች ፡ ሰውቀታቸው ፡ በፋቸው ፡ ነው ፡ ያዋ
ቆች ፡ ምክራቸው ፡ ግን ፡ በፋቸው ፡ የተናገሩት ፡
ነገር ፡ ነው ።
፳፯፤ ኃጢአተኛ ፡ ሰው ፡ እክህደክ ፡ ብሎ ፡ ሰይጣንን ፡
ቢረግመው ፡ ሰውነቱን ፡ መርገሙ ፡ ነው ።
፳፰፤ ሰው ፡ የሚያማ ፡ ሰው ፡ ሰውነቱን ፡ ያጠፋል ፡
በደረበትም ፡ ቦታ ፡ ራሱን ፡ ያስጠላል ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

፩፤ ሰነፍ ፡ ሰው ፡ በተቀመጠበት ፡ ቦታ ፡ እንደ
ዋሻ ፡ ደንጊያ ፡ ነው ፡ በጽኑ ፡ ስንፍናው ፡ ሁሉን ፡
ያቦዝናል ።
፪፤ ፫፤ ሰነፍ ፡ ሰው ፡ በተኛበት ፡ ቦታ ፡ እንደሚያጸይፍ ፡
ፈረስ ፡ ነው ። የገደለው ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ የጁን ፡
ትቢያ ፡ ማራገፉ ፡ ነው ። ያልተማረ ፡ ልጅ ፡ ላባቱ ፡
እፍረት ፡ ነው ፡ ሰነፍም ፡ ልጅ ፡ የጕስቈለች ፡
ትሆናለች ።
፬፤ ብልህ ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ባሏን ፡ ትወርሰዋለች ፡
ሰነፍ ፡ ልጅ ፡ ግን ፡ ላባቷ ፡ ኀዘን ፡ ናት ።
፭፤ ሁለጊዜ ፡ ሰባት ፡ እጥፍ ፡ ጕስቍልናን ፡ ትጐሰ
ቍላለች ፡ አባቷንም ፡ ታሳፍራለች ፡ ባሏንም ፡
ታሳፍራለች ፡ ደፋርም ፡ ናት ።
፮፤ ባገኘበት ፡ ቦታ ፡ ነገሩን ፡ የሚናገር ፡ ሰው ፡
በልቅሶ ፡ ቤት ፡ መሰንቆ ፡ እንደሚመታ ፡ ሰው ፡
ነው ። ግርፋት ፡ ከቍጣ ፡ ጋራ ፡ ሁለጊዜ ፡ ብልህ ፡
ያደርጋል ።
፯፤ ሰነፍ ፡ ሰውን ፡ የሚያስተምረው ፡ ሰው ፡ የተሰ
በረ ፡ ገልን ፡ አንድ ፡ እንደሚያደርግ ፡ ሰው ፡
ነው ፡ የተኛ ፡ ሰውን ፡ ከጽኑ ፡ እንቅልፍ ፡ ቀስቅ
ሰው ።
፰፤ ለሰነፍ ፡ ሰው ፡ የሚነግር ፡ ሰው ፡ ለተኛ ፡ ሰው ፡
እንደሚነግር ፡ ሰው ፡ ነው ፡ ነግረኸው ፡ ከጨረ
ስህ ፡ በኋላ ፡ ምን ፡ ተናገርህ ፡ ይልሃል ።
፱፤ ተድላ ፡ ደስታው ፡ አልኖልና ፡ ለሞተ ፡ ሰው ፡
አልቅስለት ፡ አእምሮው ፡ ጠፍቷልና ፡ ለሰነፍ ፡
ሰውም ፡ አልቅስለት ።
፲፤ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ አይመለስምና ፡ ለሞተ ፡ ሰው ፡
ታለቅስለት ፡ ዘንድ ፡ አገባብ ፡ ነው ። ከመሞቱ ፡
መኖሩ ፡ ይከፋበታልና ፡ ለሰነፍ ፡ ሰው ፡ ግን ፡
በሕይወት ፡ሳለ ፡ አልቅስለት ።
፲፩፤ ለሰነፍ ፡ ኃጢአተኛ ፡ በሕይወት ፡ በኖረበት ፡
ዘመን ፡ ሁሉ ፡ አልቅስለት ።
፲፪፤ ከሰነፍ ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ ነገር ፡ አታብዛ ፡ አእምሮ ፡
ከሌለውም ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ አትኑር ፡ ወደ ፡
መከራ ፡ እንዳያገባህ ፡ አንተም ፡ በሱ ፡ ስንፍና ፡
እንዳትነቀፍ ፡ ተጠበቅ ።
፲፫፤ ከሱ ፡ ራቅ ፡ ሰውነትህም ፡ ታርፋለች ፡ ይቀል
ሃል ፡ በሱ ፡ ስንፍናም ፡ አንተ ፡ የምትጎዳው ፡
የለም ።
ከአረር ፡ የሚከብድ ፡ ምን ፡ አለ ፡ ሰነፍ ፡ ከመባ ፲፬፤
ልስ ፡ በቀር ፡ የሚከፋ ፡ ምን ፡ አለ ።
ከሰነፍ ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ ከመኖር ፡ ጨውና ፡ አሸዋ ፡ ፲፭፤
የብረት ፡ ወገን ፡ ናስንም ፡ ብትሸከም ፡ ይሻላል ።
ማገሩ ፡ ያማረ ፡ በክብ ፡ ላይ ፡ ያለ ፡ ክቡ ፡ በት ፲፮፤
ናደ ፡ ጊዜ ፡ ማገሩ ፡ እንዳይፈታ ፡ ያዋቂ ፡ ሰው ፡
ምክርም ፡ በጽኑዕ ፡ ልቡና ፡ እንደሱ ፡ ነው ።
ሁለጊዜ ፡ ጽናቱ ፡ አይጠፋም ፡ ያዋቂ ፡ ሰው ፡ ፲፯፤
ምክርና ፡ በአእምሮ ፡ የጸና ፡ ልቡና ፡ ምሳሌያ
ቸው ፡ ይሎና ፡ ማገር ፡ ነው ፡ በግድግዳ ፡ ላይ ፡
ያሸዋ ፡ ምርግ ፡ እየተቀረፈ ፡ እንዲወድቅ ።
በነፋስ ፡ ፊት ፡ ያለ ፡ ገለባም ፡ ነፋስ ፡ በነፈሰ ፡ ፲፰፤
ጊዜ ፡ እንዳይቆም ፡ የሰነፍ ፡ ሰውም ፡ አሳብ ፡
የሰደበው ፡ ሰው ፡ ቢኖር ፡ ቆሞ ፡ በማይዋጋ ፡
በፈሪ ፡ ሰው ፡ ልቡና ፡ ዘንድ ፡ እንደሱ ፡ ነው ።
ዓይኑን ፡ የጠነቈሉት ፡ ሰው ፡ እንባውን ፡ ያወር ፲፱፤
ዳል ፡ ልቡናውንም ፡ በትምህርት ፡ የነካ ፡ ሰው ፡
ጥበብን ፡ ያሳያል ።
በወፎች ፡ ደንጊያ ፡ የወረወረባቸው ፡ ሰው ፡ ያባ ፳፤
ርራቸዋል ፡ በወዳጁም ፡ የሚለገድ ፡ ሰው ፡ ወን
ድሜ ፡ ወንድሜ ፡ ማለትን ፡ አጠፋ ።
በወዳጅህ ፡ ሰይፍን ፡ ብትመዝ ፡ አፍህንም ፡ ፳፩፤
በሱ ፡ ከፍና ፡ ዝቅ ፡ አድርገህ ፡ ብትናገር ፡
ወዳጅ ፡ እንደሚሆንህ ፡ መጠን ፡ ተስፋ ፡ አትቈ
ርጥለትም ።
ብትለገድበት ፡ አፍህንም ፡ በሱ ፡ ከፍና ፡ ዝቅ ፡ ፳፪፤
አድርገህ ፡ ብትናገር ፡ ብትሰድበው ፡ ምክሩንም ፡
ብታወጣበት ፡ ብትከዳው ፡ ብታሳዝነውም ፡
ነው ፡ እንጂ ፡ ወዳጅ ፡ እንደሚሆንህ ፡ መጠን ፡
ተስፋ ፡ አትቈርጥለትም ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ ወዳጅ ፡
ሁሉ ፡ ይሸሻል ።
አንተም ፡ ድሀ ፡ ብትሆን ፡ በተድላው ፡ በደስ ፳፫፤
ታው ፡ ጊዜ ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ ደስ ፡ ይልህ ፡ ዘንድ ፡
ከባልንጀራህ ፡ ጋራ ፡ ሃይማኖትህን ፡ ጠብቅ ፡
ርስቱን ፡ ባገኘ ፡ ጊዜ ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ ደስ ፡ ይልህ ፡
ዘንድ ፡ ቢቸገርም ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ መከራውን ፡
ታገሥ ።
የእሳት ፡ የጪሱ ፡ ትንታ ፡ ይቀድማል ፡ እንደ ፳፬፤
ዚሁ ፡ ደም ፡ ከማፍሰስም ፡ ጠብና ፡ ክርክር ፡ ይቀ
ድማል ።
ወዳጄን ፡ መሠወር ፡ አላፍርም ፡ ከፊቱም ፡ አል ፳፭፤
ሠወርም ።
ነገር ፡ ግን ፡ ስለሱ ፡ መከራ ፡ ብታገኘኝ ፡ የሰማ ፡ ፳፮፤
ሁሉ ፡ ከሱ ፡ ራሱን ፡ ይጠብቅ ።
ላንደበቴ ፡ ጠባቂ ፡ ማን ፡ በኖረልኝ ፡ በነሳቸው ፡ ፳፯፤
እንዳልጠፋ ፡ አንደበቴም ፡ እንዳትገድለኝ ፡ በን
ደበቴ ፡ የጥበብን ፡ ቍልፍ ፡ ማን ፡ በኖረልኝ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፫ ።

አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ አባቴ ፡ ድኅነቴን ፡ የምታደ ፩፤
ርግልኝ ፡ ፈጣሪዬ ፡ በነሳቸው ፡ ምክር ፡ አትጣ
ለኝ ፡ በነሳቸውም ፡ እጠፋ ፡ ዘንድ ፡ አትለየኝ ።

፪፤ ልቡናዬን ፡ ማን ፡ በመከረልኝ ፡ ድንቁርናዬ ፡
ይተወኝ ፡ ዘንድ ፡ በተናገሩትም ፡ ነገር ፡ ድል ፡
እንዳይነሱኝ ፡ ለልቡናዬ ፡ ጥበብን ፡ ማን ፡ ባስ
ተማረኝ ።
፫፤ በደሌ ፡ እንዳይበዛብኝ ፡ ኃጢአቴም ፡ እንዳይበ
ዛብኝ ፡ በጠላቶቼም ፡ ፊት ፡ እንዳልወድቅ ። ጠላ
ቶቼም ፡ በኔ ፡ ጥፋት ፡ ደስ ፡ እንዳይላቸው ፡ ለል
ቡናዬ ፡ ጥበብን ፡ ማን ፡ ባስተማረኝ ።
፬፤ ጌታዬ ፡ ያቤቴ ፡ ፈጣሪ ፡ ዓይኔን ፡ የሚያስታትን ፡
ነገርን ፡ አታምጣብኝ ።
፭፤ ክፉ ፡ ፈቃድንም ፡ ከኔ ፡ አርቅልኝ ።
፮፤ ጥጋብ ፡ አይምጣብኝ ፡ ቍንጣንም ፡ አያቀናጣኝ ፡
ለክፉ ፡ ሰውነትም ፡ አሳልፈህ ፡ አትስጠኝ ።
፯፤ ልጆቼ ፡ ባንደበቴ ፡ የመከርኋችሁን ፡ ምክር ፡
ስሙኝ ፡ ቃሌን ፡ የጠበቀ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ በመከራ ፡
አይሰነካከልም ፡ አንደበቱንም ፡ የጠበቀ ፡ ሰው ፡
በመከራ ፡ አይወድቅም ።
፰፤ ትዕቢተኛ ፡ ኃጢአተኛ ፡ ተሳዳቢ ፡ በነሳቸው ፡
ይጠፋሉ ።
፱፤ ልጄ ፡ ላፍህ ፡ መሐላን ፡ አታስለምደው ፡ በማል
ክም ፡ ጊዜ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ በሐሰት ፡
አትጥራ ።
፲፤ ሁልጊዜ ፡ እየመረመሩ ፡ የሚገርፉት ፡ ባሪያ ፡
ቍስሉ ፡ እንዳይደርቅ ፡ ሲምል ፡ እንደዚሁ ፡
ሁልጊዜ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ በሐሰት ፡
የሚጠራ ፡ ሰው ፡ ከመቅሠፍት ፡ አይነጻም ።
፲፩፤ የማለኛ ፡ ሰው ፡ ኃጢአቱ ፡ ብዙ ፡ ነው ፡ የወገ
ኑም ፡ መቅሠፍት ፡ አይፈጽምም ፡ ቢያረድም ፡
ኃጢአቱ ፡ አይተወውም ፡ ቸልም ፡ ቢል ፡ ኃጢ
አቱ ፡ እጥፍ ፡ ይሆንበታል ። በወገኑ ፡ ፍዳ ፡ መል
ቷልና ፡ በማላ ፡ ገንዘብ ፡ አይከብርም ።
፲፪፤ ሞትን ፡ የምታመጣው ፡ ቃል ፡ አለች ፡ በያዕ
ቆብ ፡ ርስት ፡ አትኖርም ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ በደጋ
ጎች ፡ ሰዎች ፡ ዘንድ ፡ የለም ፡ በኃጢአቱም ፡
አይሰነካከሉም ።
፲፫፤ በውስጡ ፡ ብዙ ፡ ኃጢአት ፡ አለና ፡ ካንደበትህ ፡
የመዘባበት ፡ ነገር ፡ አይውጣ ።
፲፬፤ እናትና ፡ አባትህን ፡ አስባቸው ፡ መኳንንቶችህ
ንም ፡ አገልግል ፡ በፊታቸውም ፡ አትሳት ፡ ባል
ተወለድኩ ፡ እንዳትል ፡ የተወለድህበትን ፡ ቀን ፡
እንዳትረግም ፡ በስንፍናህ ፡ እንዳትጠላ ፡ ሁን ።
፲፭፤ በሕይወት ፡ ሳለ ፡ ዝብበት ፡ የለመደ ፡ ሰው ፡ አይ
ራቀቅም ።
፲፮፤ ኃጢአትን ፡ የሚያመጡት ፡ ሁለት ፡ ናቸው ፡
ሦስተኛው ፡ ግን ፡ ሞትን ፡ ያመጣል ፡ እንደ ፡
እሳት ፡ የምትናደድ ፡ የቍጣ ፡ ሰው ፡ ሰውነት ፡
በኃጢአት ፡ ባሕር ፡ እስክታሰጥመው ፡ ድረስ ፡
አትበርድም ፡ በሰውነቱም ፡ የሚሰስን ፡ ሰው ፡
ኃጢአትን ፡ እስኪሠራት ፡ ድረስ ፡ ደርሶ ፡ አይ
ተውም ።
፲፯፤ ለሴሰኛ ፡ ሰው ፡ እህሉ ፡ ሁሉ ፡ ይጣፍጠዋል ፡ እስ
ኪሞትም ፡ ድረስ ፡ አያርፍም ።
፲፰፤ ሚስቱን ፡ ትቶ ፡ የሚሄድ ፡ ሰው ፡ መንደሩ ፡
ጨለማ ፡ ነው ፡ የሚያየኝ ፡ የለም ፡ አጥር ፡ ይጋ
ርደኛል ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ምን ፡ እፈራለሁ ፡ እግ
ዚአብሔርም ፡ ኃጢአቴን ፡ ይዘነጋልኛል ፡ እኔ
ንም ፡ በመዓት ፡ አያስበኝም ፡ ይላል ።
ነገር ፡ ግን ፡ እንዳየው ፡ የሰው ፡ ዓይን ፡ ይፈራል ፡ ፲፱፤
እልፍ ፡ ፀሐይ ፡ የለም ፡ እንጂ ፡ የእግዚአብሔ
ርም ፡ ዓይን ፡ ከዚያ ፡ እንዲበራ ፡ የሰውንም ፡
ሥራ ፡ ሁሉ ፡ እንዲያይ ፡ ሰው ፡ ተሠውሮ ፡ የሚ
ሠራውን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ እንዲያውቅ ፡ አያው
ቅም ።
ኃጢአት ፡ ሠርቶ ፡ ከጨረሰ ፡ በኋላ ፡ እንዲህ ፡ ፳፤
ያደርገዋል ።
በገርም ፡ መከከል ፡ ይበቀለዋል ፡ ያላሰበውም ፡ ፳፩፤
ጠላት ፡ ያጠፋዋል ።
ባሏን ፡ ትታ ፡ የምትሄድም ፡ ሴት ፡ እንደሱ ፡ ፳፪፤
ናት ፡ ከውሽማዋ ፡ ልጅ ፡ ትወልዳለች ።
በእግዚአብሔር ፡ አንዲት ፡ ክህደት ፡ አደረገች ፡ ፳፫፤
ሁለተኛም ፡ ባሏን ፡ ወነጀለችው ፡ ሦስተኛም ፡
በሴሰኝነቷ ፡ ሰረቀች ፡ ከውሽማዋም ፡ ልጅ ፡ ወለ
ደች ።
እንዲህ ፡ ያለችቱን ፡ ሴት ፡ ያጕሰቍሏታል ፡ ፳፬፤
በልጆቿም ፡ ትገረፋለች ።
የልጅ ፡ ልጆቿና ፡ ልጆቿ ፡ ይጠፋሉ ፡ ልጆቿም ፡ ፳፭፤
ልጅ ፡ አይወልዱም ።
ስም ፡ አጠራሯም ፡ የተረገመ ፡ ይሆናል ፡ ወገኖ ፳፮፤
ቿንም ፡ ታስረግማቸዋለች ፡ እርግማኗ ፡ ጕስቍ
ልናዋ ፡ ፈጽሞ ፡ አይጠፋም ።
ያዩት ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ከመፍራት ፡ ፳፯፤
የሚበልጥ ፡ እንደሌለ ፡ የእግዚአብሔርንም ፡
ሕግ ፡ ከመጠበቅ ፡ የሚሻል ፡ እንደሌለ ፡ ያው
ቃል ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

ወላድ ፡ ሰውነቷን ፡ በተዋሕዶ ፡ ታከብራለች ፡ ፩፤
በአሕዛብም ፡ መከከል ፡ ትመካለች ።
በእግዚአብሔርም ፡ ወገኖች ፡ መከከል ፡ ነገር ፡ ፪፤
ትናገራለች ፡ በሐዋርያትም ፡ መከከል ፡ ትመካ
ለች ።
እኔ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ አብ ፡ ተወለድሁ ፡ ምድ ፫፤
ርንም ፡ እንደ ፡ ጉም ፡ ሸፈንኋት ።
እኔ ፡ በሰማይ ፡ኖርሁ ፡ ዙፋኔንም ፡ በደመና ፡ ፬፤
ላይ ፡ ዘረጋሁ ።
ብቻዬንም ፡ በአድማስ ፡ ዞርሁ ፡ በውቅያኖስ ፡ ፭፤
መከከል ፡ ዞርሁ ።
በባሕርም ፡ ማዕበል ፡ መከከል ፡ በየብስም ፡ መከ ፮፤
ከል ፡ ተመላለስሁ ፡ ከምስት ፡ ሺ ፡ አምስት ፡
መቶ ፡ ዘመን ፡ አስቀድሞ ፡ የሕዝቡንና ፡ የአ
ሕዛቡን ፡ ሥጋ ፡ አልተዋሐድሁም ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ እረፍትን ፡ ፈለግሁ ፡ እንግዴህስ ፡ ፯፤
የማንን ፡ ሥጋ ፡ እዋሐዳለሁ ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ሁሉን ፡ የፈጠረ ፡ አብ ፡ አዘዘኝ ፡ ፰፤
ሁሉን ፡ የፈጠረ ፡ አብ ፡ ሥጋን ፡ አዋሐደኝ ፡
የያዕቆብን ፡ ሥጋ ፡ ተዋሐጂ ፡ ከእስራኤልም ፡
በነሳሽው ፡ ሥጋ ፡ ሁሉን ፡ ግዢ ፡ አለኝ ።
ዓለም ፡ ሳይፈጠር ፡ ወለደኝ ፡ ለዘለዓለሙም ፡ ፱፤

ፈጽሜ ፡ ከሱ ፡ አልለይም ።
፲፤ በሱ ፡ ፈቃድ ፡ በከበረ ፡ በማርያም ፡ ማኅበን ፡
ሥጋን ፡ ተዋሕድኩ ፡ በምክራብም ፡ አስተማ
ርኩ ።
፲፩፤ በቤተ ፡ መቅደስም ፡ እንደዚሁ ፡ አስተማርኩ ፡
አብ ፡ ባስገዛኝ ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ ወንጌልን ፡
አስተማርኩ ።
፲፪፤ ቡብዙ ፡ የእግዚአብሔር ፡ አብ ፡ ርስት ፡ እድል ፡
በሆኑ ፡ በሐዋርያት ፡ መካከል ፡ ቀዳማዊነቴን ፡
አስተማርኩ ።
፲፫፤ በደጋ ፡ እንዳለ ፡ ዝግባ ፡ ከፍታዬን ፡ ገለጥሁ ፡
በኤርሞን ፡ ተራራ ፡ እንዳለ ፡ ሰኖባርም ፡ ገነንሁ ።
፲፬፤ በውኃ ፡ ዳር ፡ እንዳለ ፡ ዘምባባም ፡ ከበርኩ ፡
በኢያሪኮ ፡ እንዳለ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡
እንዳለች ፡ እንዳማረች ፡ እንደ ፡ ዘይት ፡ እንጨ
ትም ፡ መዓዛ ፡ ትምርቴ ፡ ያማረ ፡ የተወደደ ፡
ሆን ፡ እንደ ፡ ሰውዝና ፡ እንደ ፡ ገውዝም ፡ ገነ
ንሁ ፡ ከበርሁ ።
፲፭፤ መዓዛ ፡ ትምርቴም ፡ ደርሰኔ ፡ እንደሚባል ፡ ቀሰ
ፊደሬራም ፡ እንደሚባል ፡ ሽቱ ፡ ያማረ ፡ የተወ
ደደ ፡ ሆን ፡ እንዳማረ ፡ ሽቱ ፡ መዓዛ ፡ መዓዛ ፡ ትም
ርቴ ፡ እንደዚያ ፡ የተወደደ ፡ ሆን ፡ እንደልባንጃ ፡
እንደ ፡ ጥርኝ ፡ ሚዓ ፡ እንደሚባል ፡ ሽቱ ፡ በደ
ብተራ ፡ አረት ፡ እንዳለ ፡ እንደ ፡ ነጭ ፡ ዕጣን ፡
መዓዛም ፡ መዓዛ ፡ ትምርቴ ፡ እንደዚያ ፡ የተወ
ደደ ፡ ሆን ።
፲፮፤ ደቀ ፡ መዛሙርቶቼ ፡ ሐዋርያትም ፡ እንደ ፡
ቡጥም ፡ ከበሩ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቴ ፡ ሐዋርያት ፡
ጌትነትና ፡ ክብር ፡ ያላቸው ፡ ደቀ ፡ መዛሙር
ቶች ፡ ናቸው ።
፲፯፤ እኔስ ፡ እንደ ፡ ተወደደ ፡ ወይን ፡ ሐረግ ፡ መወ
ደድን ፡ አገኘሁ ።
፲፰፤ ትምርቴም ፡ ጌትነትና ፡ ክብር ፡ መወደድና ፡
ባለጸግነት ፡ ያለው ፡ ትምርት ፡ ነው ።
፲፱፤ ስም ፡ አጠራሬ ፡ ከማር ፡ ይልቅ ፡ ይጣፍጣልና ፡
ርስትነቴም ፡ ከሸንከር ፡ ይልቅ ፡ ይጣፍጣልና ።
፳፤ የምትወዱኝ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ወደኔ ፡ ኑ ፡ ትም
ርቴንም ፡ ትማራላችሁ ።
፳፩፤ ትምርቴን ፡ የሚማሩ ፡ ሰዎች ፡ አይሰለቹኝም ፡
ሥጋዬንም ፡ የሚቀበሉ ፡ ሰዎች ፡ አይሰለቹ
ኝም ።
፳፪፤ የሚሰማኝ ፡ መከራ ፡ መጥቶበት ፡ አያፍርም ፡
ለኔ ፡ የሚገዙ ፡ ሰዎች ፡ አይስቱም ።
፳፫፤ ይህ ፡ ሁሉ ፡ ሙሴ ፡ ያዘዘን ፡ የእግዚአብሔር ፡
ሕግ ፡ የያዕቆብም ፡ ወገኖች ፡ ርስት ፡ በተጻ
ፈበት ።
፳፬፤ መጽሐፍ ፡ ተጽፏል ።
፳፭፤ ጥበብን ፡ እንደ ፡ ኤፌሶን ፡ ፈሳሽ ፡ በሚያዝያም ፡
ወራት ፡ እንደሚመላ ፡ እንደ ፡ ጤግሮስ ፡ ፈሳሽ ፡
በሰው ፡ ልቡና ፡ የሚመላት ፡ እሱ ፡ ነው ።
፳፮፤ ምክርንም ፡ የኤፍራጥስ ፡ ፈሳሽ ፡ በዝመራም ፡
ወራት ፡ የዮርዳኖስ ፡ ፈሳሽ ፡ እንዲመላ ፡ በሰው ፡
ልቡና ፡ የሚመላት ፡ እሱ ፡ ነው ።
፳፯፤ የዓባይ ፡ ፈሳሽ ፡ በወይን ፡ አዝመራ ፡ ወራት ፡
እንዲመላ ፡ ጥበብንም ፡ እንደ ፡ ብርሃን ፡ የሚገ
ልጣት ፡ እሱ ፡ ነው ።
አዳም ፡ ፈጽሞ ፡ አላወቃትም ፡ ጴጥሮስም ፡ ፳፰፤
ምሥጢርዋን ፡ መርምሮ ፡ አላወቀም ።
ምሥጢሯ ፡ ከባሕር ፡ ውኃ ፡ ይልቅ ፡ ይበዛል ፡ ፳፱፤
ምክሯም ፡ ከባሕሩ ፡ ጥልቅ ፡ ይልቅ ፡ ይረቃል ።
እውቀቱም ፡ በወንዝ ፡ እንደሚፈስ ፡ ፈሳሽ ፡ ፴፤
በዛልኝ ፡ የመስኖ ፡ ውኃ ፡ ወደ ፡ ተክል ፡ እንዲ
ገባ ፡ በእስራኤል ፡ አደርሁ ።
የሕጌ ፡ ማደሪያ ፡ ምዕመናን ፡ አስተምራቸው ፡ ፴፩፤
ዘንድ ፡ ላስተምራቸው ፡ አልሁ ፡ እውቀቴ ፡
እንደ ፡ ውኃ ፡ በዛልኝ ፡ እውቀቴም ፡ እንደ ፡
ባሕር ፡ ሆነልኝ ።
ዳግመኛም ፡ ጥበብን ፡ እንደ ፡ ብርሃን ፡ ቀጥዬ ፡ ፴፪፤
ቀጥዬ ፡ በሰው ፡ ልቡና ፡ አበራታለሁ ፡ ወንጌል
ንም ፡ እስከ ፡ ዕለተ ፡ ምጽአት ፡ ድረስ ፡ አስተ
ምራታለሁ ።
የሙሴ ፡ ሀብት ፡ በኢያሱ ፡ እንዳደረ ፡ ትምር ፴፫፤
ትን ፡ በሰው ፡ ልቡና ፡ አሳድራታለሁ ፡ ለዘላ
ለሙ ፡ ለልጅ ፡ ልጅም ፡ አጸናታለሁ ።
ለሚፈልጉኝ ፡ ሰዎችም ፡ ሁሉ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ፴፬፤
የደከምሁ ፡ ለኔ ፡ ብቻ ፡ እንዳይደለ ፡ እነሆ ፡ እዩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፭ ።

በነዚህ ፡ በሦስቱ ፡ ነገሮች ፡ ደስ ፡ አለኝ ፡ በሰ ፩፤
ውና ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ደግ ፡ ሰው ፡
ሆኜ ፡ ጸናሁ ፡ በንድ ፡ ልብ ፡ የሚተባበሩ ፡ ወን
ድማቾች ፡ የተደነቁ ፡ ናቸው ። ወንድሜ ፡ ወን
ድሜ ፡ የሚባበሉ ፡ ወዳጆችም ፡ የተደነቁ ፡
ናቸው ። ከሚስቱም ፡ ጋራ ፡ በሥራ ፡ የተባበረ ፡
ሰው ፡ የተደነቀ ፡ ነው ።
ከንቱ ፡ የሆኑ ፡ ሦስት ፡ ነገሮችን ፡ ሰውነቴ ፡ ፪፤
ናቀች ፡ ፈጽማም ፡ ጠላቻቸው ፡ ኑሯቸውም ፡
አበሳጩችኝ ፡ ትዕቢተኛ ፡ ድሀን ፡ ንፉግ ፡ ባለጸ
ጋን ፡ ሴሰኛ ፡ አእምሮ ፡ የሌለው ፡ ሽማግሌንም ፡
እነዚህን ፡ ሦስቱን ፡ ጠላሁ ።
ከሕፃንነትህ ፡ ጀምረህ ፡ ያልተመከርህ ፡ በርጅ ፫፤
ናህ ፡ ጊዜ ፡ እንዴት ፡ ብልህ ፡ ትሆናለህ ።
ለሺበትህ ፡ ባንተ ፡ መፍረድ ፡ ይገባዋል ፡ ላለቆ ፬፤
ችም ፡ ምክር ፡ ይገባቸዋል ።
ለሽማግሎችም ፡ ጥበብ ፡ ይገባቸዋል ፡ ለመኳን ፭፤
ንትም ፡ ጥበብን ፡ መማር ፡ ይገባቸዋል ።
የትምህርት ፡ ብዛት ፡ ለሽማግሎች ፡ ዘውዳቸው ፡ ፮፤
ነው ፡ መመኪያቸውም ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍ
ራት ፡ ነው ።
በልቤ ፡ ያደነቅኋቸው ፡ ዘጠኝ ፡ ነገሮች ፡ ናቸው ፡ ፯፤
አሥረኛውን ፡ ግን ፡ በቃሌ ፡ እናገራለሁ ፡ በል
ጆቹ ፡ ደስ ፡ የሚለው ፡ በሕይወትም ፡ ሳለ ፡ የጠ
ላቱን ፡ ጥፋት ፡ የሚያይ ፡ ሰው ፡ የተደነቀ ፡ ነው ።
ልባም ፡ ሴት ፡ ያገባ ፡ ሰው ፡ የተደነቀ ፡ ነው ፡ ፰፤
በቃሉ ፡ ያልሳተ ፡ በጠላቱም ፡ እጅ ፡ ያልወደቀ ፡
ሰው ፡ የተደነቀ ፡ ነው ።
ጥበብን ፡ ያገኛት ፡ የሚታዘዝለትም ፡ ያገኘ ፡ ፱፤
ሰው ፡ የተደነቀ ፡ ነው ።

፲፤ መንፈሳዊ ፡ ጥበብን ፡ ያገኘ ፡ ደግ ፡ ሰው ፡ ነው ፡
ነገር ፡ ግን ፡ ይህንን ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍ
ራት ፡ ይበልጠዋል ።
፲፩፤ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ ከሁሉ ፡ ትልቃ
ለች ።
፲፪፤ እሷን ፡ የጠበቀ ፡ ሰውን ፡ የሚመስለው ፡ የለም ።
፲፫፤ ከቍስል ፡ ሁሉ ፡ የልብ ፡ ቍስል ፡ ይከፋል ፡ ከክ
ፋት ፡ ሁሉ ፡ ደረቅ ፡ ሴት ፡ ትከፋለች ።
፲፬፤ በሁሉ ፡ ብትወድቅ ፡ በዘገየው ፡ ጠላትህ ፡ እጅ ፡
አትውደቅ ፡ ሁሉ ፡ ቢቀየምህ ፡ ጥንት ፡ ጠላ
ትህ ፡ አይቀየምህ ።
፲፭፤ ከምድር ፡ እባብ ፡ ራስ ፡ የሚከፋ ፡ የለም ፡ ከጥ
ንት ፡ ጠላትም ፡ ቂም ፡ የሚከፋ ፡ የለም ።
፲፮፤ ከደረቅ ፡ ሴት ፡ ጋራ ፡ ከትኖር ፡ ከምድር ፡ አው
ሬዎችና ፡ ከአንበሳዎች ፡ ጋራ ፡ መኖር ፡ ይሻ
ላል ።
፲፯፤ ክፋቷ ፡ መልኳን ፡ ይለውጠዋል ፡ ፊቷንም ፡
እንደ ፡ ግስላ ፡ ለምድ ፡ ያጠቍረዋል ።
፲፰፤ ባሏንም ፡ በባልንጀሮቹ ፡ ማህል ፡ ይንቁታል ፡
ጽኑ ፡ አዘንንም ፡ ያሳዝኑታል ፡ ችክ ፡ ምንችክ ፡
አድርገው ፡ ይይዙታል ።
፲፱፤ ከደረቅ ፡ ሴት ፡ ክፋት ፡ ሁሉ ፡ ታንሳለች ፡ እሷም ፡
ወደ ፡ ኃጢአት ፡ እድል ፡ ታደርሳለች ።
፳፤ የድቡሽት ፡ አቀበት ፡ ሽማግሌዎችን ፡ እግራቸ
ውን ፡ እንዲያደክማቸው ፡ ቀበጣሪ ፡ ሴት ፡ እን
ደዚሁ ፡ የዋህ ፡ ሰውን ፡ ታደክመዋለች ።
፳፩፤ መቅሠፍት ፡ ናትና ፡ ጥፋትም ፡ ናትና ፡ ጽኑ ፡
ውርደትም ፡ ናትና ፡ የሴት ፡ መልኳ ፡ አያስትህ ፡
ሴት ፡ ኃፍረቷን ፡ ሽጣ ፡ ባሏን ፡ ብትመግበው ፡
እፍረት ፡ ነው ።
፳፪፤ የልብ ፡ ቍስል ፡ ናት ፡ ፊትም ፡ ታጠቍራለች ፡
ደረቅ ፡ ሴት ፡ የነፍስ ፡ ኀዘን ፡ ናት ፡ እንደዚሁ ፡
ባሏን ፡ እማታከብር ፡ ሴት ፡ ልምሾ ፡ እንደ ፡
ሆነ ፡ እግርና ፡ እንደ ፡ ደካማ ፡ እጅ ፡ ናት ።
፳፫፤ ጥንቱንም ፡ ኃጢአት ፡ ከሴት ፡ ተገኘች ፡ ስለ
ሷም ፡ ሁላችን ፡ እንሞታለን ።
፳፬፤ በቤት ፡ አጠገብ ፡ ለውኃ ፡ መፍሰሻ ፡ አታብጅ
ለት ፡ ለሴትም ፡ የልብህን ፡ ምሥጢር ፡ አታው
ጣላት ።
፳፭፤ ግብሯ ፡ እንደ ፡ ግብርህ ፡ ካልሆነች ፡ ፍታት ፡
ከሰውነትህም ፡ ለያት ።

ምዕራፍ ፡ ፳፮ ።

፩፤ ደግ ፡ ሴትን ፡ ባሏ ፡ ያደንቃታል ፡ በሕይወት ፡
የሚኖርበትም ፡ ዘመን ፡ እጥፍ ፡ ይሆናል ።
፪፤ የበሬ ፡ ወገን ፡ የሆነች ፡ ሴት ፡ ባሏን ፡ ደስ ፡ ታሰ
ኘዋለች ፡ ዘመኑንም ፡ በተድላ ፡ በደስታ ፡ ይጨ
ርሳል ።
፫፤ የደግ ፡ ሴት ፡ እድሏ ፡ ያማረ ፡ ነው ፡ እግዚአብ
ሔርን ፡ የሚፈራ ፡ ሰውንም ፡ ወደ ፡ እድሉ ፡
ታደርሰዋለች ።
፬፤ የባለጸጋውም ፡ የደኃውም ፡ ልቡ ፡ ያማረ ፡ ይሁን ፡
ሁለጊዜም ፡ ፊቱ ፡ የበራ ፡ ይሁን ።
፭፤ በነዚህ ፡ በሦስቱ ፡ ነገሮች ፡ ልቡናዬ ፡ ደነገጠ
ብኝ ፡ አራተኛውም ፡ ልቡናዬን ፡ አስፈራኝ ፡
ይኸውም ፡ ያገር ፡ ወንጀል ፡ የአሕዛብ ፡ መሰብ
ሰብ ፡ ሰውን ፡ ለሞት ፡ የሚያደርስ ፡ አሰተኛ ፡
ምስክር ፡ ነው ።
ባሏን ፡ ከውሽማዋ ፡ ጋራ ፡ የምታቃና ፡ ሴት ፡ ፮፤
የልብ ፡ ቍስል ፡ ናት ፡ የሰውነትም ፡ ኀዘን ፡ ናት ፡
በመከራው ፡ ሁሉ ፡ የነገረ ፡ ሠሪ ፡ አንደበት ፡
ከመጣው ፡ ግርፋት ፡ ጋራ ፡ ትተከከላለች ።
ደረቅ ፡ ሴት ፡ ውልቅ ፡ ውልቅ ፡ እንደሚል ፡ ፯፤
እንደ ፡ በሬ ፡ ቀምበር ፡ ናት ፡ ከሷም ፡ ጋራ ፡ የሚ
ኖር ፡ ሰው ፡ ጊንጥ ፡ እንደሚጨብጥ ፡ ሰው ፡ ነው ።
አፍረቷን ፡ የማትሸፍን ፡ ሰካር ፡ ሴት ፡ ጽኑ ፡ ፰፤
ጥፋት ፡ ናት ።
የሴት ፡ ዝሙቷ ፡ በይኗ ፡ ይታወቃል ፡ በቅን ፱፤
ድቧም ፡ ይታወቃል ።
ስታ ፡ ራሷን ፡ እንዳታጠፋ ፡ ልጅህን ፡ አጥንተህ ፡ ፲፤
ጠብቃት ።
የሚገዳህ ፡ ነገር ፡ ቢኖር ፡ ትጸጸት ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ፲፩፤
መጸጸት ፡ እንዳትመለስ ፡ ከባሏም ፡ ፈቃድ ፡
እንዳትወጣ ፡ አድርግ ።
የተጠማ ፡ ሰው ፡ ጭቃውን ፡ እንዲልስ ፡ ከቀረበ ፲፪፤
ውም ፡ ውኃ ፡ እንዲጠጣ ፡ በእንጨት ፡ ሥርም ፡
እንዲያርፍ ።
አርበኛም ፡ ፍላፃውን ፡ ከጐራንጕሬው ፡ ፈጥኖ ፡ ፲፫፤
እንዲያወጣ ፡ ሴሰኛ ፡ ሴትም ፡ ከቤቷ ፡ መዘገ
ብላ ፡ ፈጥና ፡ ትወጣለች ።
የሴት ፡ መወደዷ ፡ ባሏን ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ። ፲፬፤
ጥበቧም ፡ ሰውነቱን ፡ ያድሰዋል ። ፲፭፤
የዋህ ፡ ሴት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እድሉ ፡ ናት ። ፲፮፤
ለብልህ ፡ ሴት ፡ ለውጥ ፡ የላትም ። ፲፯፤
ሰውና ፡ እግዚአብሔርን ፡ የምታፍር ፡ ሴት ፡ በበ ፲፰፤
ረከት ፡ ላይ ፡ በረከትን ፡ ታገኛለች ።
ነገር ፡ ለምትታገሥ ፡ ሴት ፡ ለውጥ ፡ የላትም ። ፲፱፤
ፀሐይ ፡ እግዚአብሔር ፡ በፈጠረው ፡ በሰማይ ፡ ፳፤
ሆኖ ፡ እንዲያበራ ፡ እንደዚሁ ፡ የደግ ፡ ሴት ፡
ጌጧ ፡ ባማረ ፡ በቤቷ ፡ ውስጥ ፡ ነው ።
የደብተራ ፡ አሪት ፡ ፋና ፡ በመቅረዟ ፡ ላይ ፡ እን ፳፩፤
ድታበራ ፡ እንደዚሁ ፡ የብልህ ፡ ሰውም ፡ ግብሩ ፡
በመልኩ ፡ ይታወቃል ።
በብር ፡ ሰከተት ፡ ላይ ፡ የቆሙ ፡ የወርቅ ፡ ምሰሶ ፳፪፤
ዎች ፡ ደስ ፡ እንዲያሰኙ ፡ በበጎ ፡ ሥራ ፡ ጸንቶ ፡
የሚኖር ፡ የደግ ፡ ሰው ፡ እግር ፡ አገባብም ፡ እን
ደዚሁ ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ።
በነዚህ ፡ በሦስቱ ፡ ነገሮች ፡ ልቡናዬ ፡ አዘነብኝ ። ፳፫፤
አራተኛው ፡ ግን ፡ ብስጭትን ፡ አመጣብኝ ። ፳፬፤
መጀመሪያ ፡ አርበኛ ፡ ጨካኝ ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ ፳፭፤
የሚበላው ፡ የሚጠጣው ፡ አጥቶ ፡ ቢቸገር ፡
ነው ።
ሁለተኛም ፡ አዋቆች ፡ የሆኑ ፡ ሰዎች ፡ ከእግዚ ፳፮፤
አብሔር ፡ ሕግ ፡ ወጥተው ፡ ቢስቱ ፡ ነው ።
ሦስተኛው ፡ ጽድቅን ፡ ትቶ ፡ ወደ ፡ ኃጢአት ፡
የሚመለስ ፡ ነው ።
እንዲህ ፡ ያለውን ፡ እግዚአብሔር ፡ በጦር ፡ ፳፯፤
ፋዋል ።

፳፱ አንጥረኛ ፡ ከኃጢአት ፡ በጭንቅ ፡ ይድናል ፡
መሸተኛም ፡ ከኃጢአት ፡ ተመልሶ ፡ አይጸድ
ቅም ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፩ ።

፩ በግብገብነት ፡ ኃጢአትን ፡ የሚሠሩዋት ፡ ብዙ ፡
ሰዎች ፡ ናቸው ፡ ገንዘቡ ፡ ይበዛ ፡ ዘንድ ፡ የሚ
ወድ ፡ ሰው ፡ ፊቱን ፡ ወደ ፡ ፍቅረ ፡ ንዋይ ፡ ይመ
ልሳል ።
፪ በቅጥር ፡ መካከል ፡ ድንኳን ፡ ይተክላሉ ፡ በንግ
ድና ፡ በዋጋም ፡ መካከል ፡ ኃጢአት ፡ ትመጣለች ።
፫ እግዚአብሔርን ፡ ፈርቶ ፡ ካልተጠበቀ ፡ የቤቱ ፡
ጥፋት ፡ አይዘገይም ።
፬ በወንጠፍት ፡ መካከል ፡ አሠር ፡ ይከማቻል ፡
እንደዚሁም ፡ ሁሉ ፡ ሰውን ፡ ኃጢአት ፡ ታገኘ
ዋለች ።
፭ የሸክላ ፡ ዕቃን ፡ እሳት ፡ ይፈትነዋል ፡ ሰውንም ፡
የልቡናው ፡ አሳብ ፡ ይፈትነዋል ።
፮ ተክል ፡ የሚጠብቅ ፡ ሰው ፡ ፍሬውን ፡ ያያል ፡
እንደዚሁም ፡ የሰው ፡ ነገሩ ፡ የልቡናውን ፡
ፈቃድ ፡ ይገልጥበታል ።
፯ ሰውን ፡ ከሥራው ፡ የተነሣ ፡ ይፈትኑታልና ፡
ሰውን ፡ ሳትጠይቅ ፡ አታድንቀው ።
፰ ጽድቅን ፡ ብትከተላት ፡ ታገኛታለህ ፡ እንደ ፡
ከበረ ፡ መሎጣ ፡ ግምጃም ፡ ትለብሳታለህ ።
፱ ወፍ ፡ ከዘመዱ ፡ ጋራ ፡ ይኖራል ፡ ጽድቅም ፡ በሚ
ሠሯት ፡ ሰዎች ፡ ዘንድ ፡ ትኖራለች ።
፲ አንበሳ ፡ የሚበላውን ፡ ያድናል ፡ ኃጢአትም ፡
የሚሠሩዋትን ፡ ሰዎች ፡ ታድናቸዋለች ።
፲፩ እውነተኛ ፡ ሰው ፡ ሁለጊዜ ፡ ጥበብን ፡ ያስተም
ራል ፡ የሰነፍ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ እውቀቱ ፡ እየነጋ ፡
እንደ ፡ ጨረቃ ፡ ይከፈልበታል ።
፲፪ በሰነፎች ፡ ዘንድ ፡ ጊዜውን ፡ ተጠበቅ ፡ በብል
ሆች ፡ ሰዎች ፡ ዘንድ ፡ ግን ፡ ሁለጊዜ ፡ ነገሩን ፡
ተረዳ ።
፲፫ የሰነፎች ፡ ነገር ፡ ያበሳጫል ፡ ሳቃቸውም ፡ የኃ
ጢአት ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ነው ።
፲፬ ብዙ ፡ መሐላን ፡ የሚምል ፡ ሰው ፡ ራስ ፡ ስቅጥጥ ፡
ስቅጥጥ ፡ ያደርጋል ። የትዕቢተኛ ፡ ሰው ፡ ክር
ክርም ፡ ገሮሮ ፡ ያደነቍራል ።
፲፭ የትዕቢተኞች ፡ ክርክራቸው ፡ ደም ፡ ያስፈስ
ሳል ፡ ክርክራቸውም ፡ ለሚሰማቸው ፡ ሰው ፡
ድካም ፡ ነው ።
፲፮ የባልንጀራውን ፡ ምሥጢር ፡ ያወጣ ፡ ሰው ፡
መታመኑን ፡ አጠፋ ፡ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ወዳጅ ፡
አያገኝም ።
፲፯ ወዳጅህን ፡ ጠብቅ ፡ ከሱም ፡ ጋራ ፡ ተማመን ፡
ምሥጢሩን ፡ ብታወጣበት ፡ ግን ፡ እንግዴህ ፡
ፈጽመህ ፡ በኋላው ፡ አትከተለውም ።
፲፰ ሰው ፡ ጠላቱን ፡ እንዳጠፋ ፡ የወዳጅህን ፡ ወን
ድሚ ፡ ወንድሚ ፡ ማለትን ፡ አጠፋህ ።
፲፱ ወፍ ፡ ከእጅህ ፡ እንድታመልጥ ፡ ወዳጅህ ፡ እን
ደዚሁ ፡ ካንተ ፡ አመለጠህ ።
፳ ሚዳቋ ፡ ከወጥመድ ፡ እንድታመልጥ ፡ ፈጽሞ ፡
አምልጦሃልና ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አትከተለውም ።
ቍስል ፡ ቢሆን ፡ ተሽሶው ፡ በዳኑት ፡ ነበር ፡ ፳፩
የተሳደበም ፡ ሰው ፡ በካከሱት ፡ ነበር ፡ የባልንጀ
ራውን ፡ ምሥጢር ፡ ያወጣውን ፡ ሰው ፡ ግን ፡
ተስፋ ፡ ይቈርጡለታል ።
ክፋቱን ፡ ማስተው ፡ የሚችል ፡ የለምና ፡ በይኑ ፡ ፳፪
የሚጠቅስ ፡ ሰው ፡ ልቡናው ፡ ያማረ ፡ አይሆ
ንም ።
ለዓይንህ ፡ ግን ፡ ከንፈሩን ፡ ይመጥልሃል ፡ በተ ፳፫
ናገርኸው ፡ ሁሉ ፡ ያመሰግንሃል ፡ ኋላ ፡ ግን ፡
በቃሉ ፡ ይወነጅልሃል ፡ በተናገርኸው ፡ ቃል ፡
ያስትሃል ።
የጠላኋቸው ፡ ሰዎች ፡ ብዙ ፡ ናቸው ፡ ነገር ፡ ፳፬
ግን ፡ እንደሱ ፡ አይደሉም ፡ እግዚአብሔርም ፡
እሱን ፡ ጠላ ።
በባልንጀራው ፡ ድንጋይ ፡ የሚወረውር ፡ ሰው ፡ ፳፭
በራሱ ፡ ላይ ፡ ትወርዳለች ፡ የበደል ፡ ግርፋት ፡
ግን ፡ ቍስል ፡ ይታወቃል ።
በባልንጀራው ፡ ጕድጓድ ፡ የቆፈረ ፡ ሰው ፡ እሱ ፡ ፳፮
በውስጡ ፡ ይወድቃል ፡ ወጥመድም ፡ ያዘጋጀ ፡
ሰው ፡ በወጥመዱ ፡ ይያዛል ።
ኃጢአት ፡ የምትመጣበትን ፡ አያውቅም ። ፳፯
የትዕቢተኞች ፡ ስድባቸው ፡ ሳቃቸው ፡ እንደ ፡ ፳፰
አንበሳ ፡ ታድናቸዋለች ፡ ተበቅላ ፡ ታጠፋቸዋ
ለች ።
በደግ ፡ ሰው ፡ ጥፋት ፡ ደስ ፡ የሚላቸው ፡ ፳፱
ሰዎች ፡ በፍዳ ፡ ይያዛሉ ፡ የሚሞቱበት ፡ ጊዜ ፡
ሳይደርስ ፡ መቅሠፍት ፡ ያጠፋቸዋል ።
ቍጣና ፡ መዓትም ፡ የሚያስጸይፉ ፡ ናቸው ፡ ፴
በኃጢአተኛ ፡ ሰውም ፡ ዘንድ ፡ ጸንተው ፡ ይኖ
ራሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳፪ ።

ለእግዚአብሔር ፡ ብሎ ፡ መከራውን ፡ ለሚታ ፩
ገሥ ፡ ሰው ፡ ጠላቱን ፡ ተበቅሎ ፡ ያጠፋለታል ፡
ኃጢአቱንም ፡ ያስተሠርይለታል ።
ባልጀራህን ፡ የምትነቅፈው ፡ ኃጢአቱን ፡ ይቅር ፡ ፪
በለው ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ከተለማመጥህ ፡ ኃጢአ
ትህን ፡ ያስተሠርይልሃል ።
አንተ ፡ ሰው ፡ ሆነህ ፡ እንዳንተ ፡ ያለውን ፡ ሰው ፡ ፫
ሳትቀየም ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንዴት ፡ ይቅር ፡
በለኝ ፡ ትለዋለህ ።
እንዳንተ ፡ ያለ ፡ ሰውን ፡ ይቅር ፡ ሳትል ፡ ኃጢአ ፬
ትህን ፡ ያስተሠርይልህ ፡ ዘንድ ፡ እንግዴህ ፡ እን
ዴት ፡ ትለምነዋለህ ።
ኃጢአትህን ፡ አስበህ ፡ ጠብን ፡ ተዋት ። ፭
ሞትን ፡ አስበው ፡ መቃብርንም ፡ አስበው ፡ ትእ ፮
ዛዙንም ፡ ጠብቅ ።
ሕጉን ፡ አስበህ ፡ ባልንጀራህን ፡ አትቀየም ፡ የእ ፯
ግዚአብሔርን ፡ ፍርዱን ፡ አስበህ ፡ ቍጣንም ፡
አርቃት ።
ቍጣን ፡ ክርክርን ፡ ተዋት ፡ ኃጢአቶችህን ፡ ፰
ታስነሣቸዋለች ፡ ቍጡ ፡ ሰው ፡ ክርክርን ፡ ያነ
ሣሣዋል ።

፱፤ ኃጢአተኛ ፡ ሰው ፡ ባልንጀራውን ፡ ያደክማል ፡
በወዳጆቹም ፡ መካከል ፡ ነገር ፡ ሥርቶ ፡ ያጣላል ።
፲፤ በእንጨቱ ፡ ልክ ፡ የእሳቱ ፡ ነዲዱ ፡ ይበዛል ፡
በክርክሩም ፡ ብዛት ፡ ልክ ፡ ጠቡን ፡ ያበዛል ፡
የሰውም ፡ ኃይሉ ፡ በቁመቱ ፡ ልክ ፡ ነው ፡ በባለ
ጸግነቱም ፡ ብዛት ፡ ልክ ፡ ቍጣውን ፡ ያበዛታል ።
፲፩፤ መታበይን ፡ የሚያበዛት ፡ ሰው ፡ ኃጢአትን ፡
ይሠራታል ፡ ለጠብ ፡ የሚቸኩል ፡ ሰው ፡ ፈጥኖ ፡
ደምን ፡ ያፈስል ።
፲፪፤ ፍምን ፡ እፍ ፡ ብትላት ፡ ትነዳለች ፡ ትፍም ፡ ብት
ልባት ፡ ትጠፋለች ፡ ሁለቱም ፡ ሁሉ ፡ ከንድ ፡
አፍ ፡ ይወጣሉ ።
፲፫፤ ብዙ ፡ ወዳጆችን ፡ አጣልቷልና ፡ አሚተኛ ፡
ላንዱ ፡ እውነት ፡ ላንዱ ፡ አሰት ፡ የሚናገርን ፡
ሰው ፡ ይረግሙታል ።
፲፬፤ ነገረ ፡ ሠሪ ፡ አንደበት ፡ ብዙ ፡ ሰዎችን ፡ አወከ
ቸው ፡ ከንዱ ፡ ወገንም ፡ ወደንዱ ፡ ወገን ፡ እንዲ
ሰደዱ ፡ አደረጋቸው ፡ ብዙ ፡ አምባዎችንም ፡
አፈረሰች ፡ የመኳንንቱንም ፡ ቤት ፡ አፈረሰች ።
፲፭፤ ቀባጣሪ ፡ አንደበት ፡ ሴቶችን ፡ ከባሎቻቸው ፡
ቤት ፡ አስወጥታ ፡ ሰደደቻቸው ፡ ገንዘባቸው
ንም ፡ አጠፋችባቸው ።
፲፮፤ ከነገረ ፡ ሠሪ ፡ አንደበት ፡ ያልተጠበቀ ፡ ሰው ፡
ግን ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ከመከራው ፡ አያርፍም ፡ በፍ
ቅርም ፡ አይኖርም ።
፲፯፤ የግርፋት ፡ ቍስል ፡ መግል ፡ ይይዛል ፡ የነገረ ፡ ሠሪ ፡
አንደበት ፡ ቍስል ፡ ግን ፡ አጥንት ፡ ይሰብራል ።
፲፰፤ በጦር ፡ ተደብድበው ፡ የወደቁ ፡ ሰዎች ፡ ብዙ ፡
ናቸው ፡ ነገር ፡ ግን ፡ በነገረ ፡ ሠሪ ፡ አንደበት ፡
እንደ ፡ ጠፉ ፡ አይደሉም ።
፲፱፤ ከሷ ፡ የዳነ ፡ በጥፋቷም ፡ ያልተሰነከከለ ፡ በሥራ
ቷም ፡ ያልጸና ፡ በግር ፡ ብረቷም ፡ ያልታሠረ ፡
የተደነቀ ፡ ነው ።
፳፤ ሥራቷም ፡ የጸና ፡ ሥራት ፡ ነው ፡ የምታመጣ
ውም ፡ መከራ ፡ ጽኑ ፡ ነው ።
፳፩፤ ሞቷም ፡ ጽኑ ፡ ሞት ፡ ነው ፡ ከሷ ፡ ሲኦል ፡ ትቀ
ላለች ።
፳፪፤ በደጋጎች ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ አትደርስባቸውም ፡ በእ
ሳት ፡ መቃጠልም ፡ አያገኛቸውም ።
፳፫፤ እግዚአብሔርን ፡ የዘነጉ ፡ ሰዎች ፡ በሷ ፡ ይጠ
ፋሉ ፡ በማይጠፋ ፡ እሳቷም ፡ ታቃጥላቸዋለች ።
እንደ ፡ አንበሳም ፡ ትወረወርባቸዋለች ፡ እንደ ፡
ነብርም ፡ ትይዛቸዋለች ።
፳፬፤ ገንዘብህን ፡ በሾህ ፡ ብታጥር ፡ ብርና ፡ ወርቅህ
ንም ፡ ብትቈልፍ ።
፳፭፤ ነገርህን ፡ መጥነህ ፡ ብትናገር ፡ በንደበትህም ፡
አርምሞን ፡ ብታኖር ፡ በማረ ፡ በተገባ ፡ ነበር ።
፳፮፤ ዳግመኛም ፡ በንደበትህ ፡ እንዳትሰነከከል ፡ በሚ
ያድንህ ፡ ጠላትህም ፡ ፊት ፡ እንዳትጥልህ ፡ ተጠ
በቅ ።

ምዕራፍ ፡ ፳፱ ።

፩፤ ምጽዋትን ፡ የሚመጸውት ፡ ሰው ፡ ለእግዚ
አብሔር ፡ በማደሩ ፡ ነው ፡ በእጁም ፡ የሚበቃ ፡
ገንዘብ ፡ ያለው ፡ ፊቃዱን ፡ ያደርጋል ።
በተድላው ፡ በደስታው ፡ ጊዜ ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ ደስ ፡ ፪፤
ይልህ ፡ ዘንድ ፡ በተቸገረ ፡ ጊዜ ፡ ለባልንጀራህ ፡
አበድረው ።
ወዳጅህን ፡ ጠብቅ ፡ ከሱም ፡ ጋራ ፡ ተማመን ፡ ፫፤
በወደድኻትም ፡ ጊዜ ፡ ጽድቅን ፡ ታገኛታለህ ።
የብድርን ፡ ገንዘብ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ወድቆ ፡ ፬፤
ያገኙት ፡ የሚመስላቸው ፡ ሰዎች ፡ ብዙ ፡ ናቸው ፡
ያበደሩዋቸውን ፡ በመከራቸውም ፡ ጊዜ ፡ የረ
ዱቸውን ፡ በለጸጎች ፡ አደከሟቸው ።
እስኪበደርህ ፡ ድረስ ፡ ራስህን ፡ ይስምሃል ፡ ቃሉ ፭፤
ንም ፡ ያደክማል ፡ ገንዘብህንም ፡ እስኪወስድ ፡
ድረስ ፡ ያባብልሃል ፡ በተከፈልከው ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡
ቀጠሮህን ፡ ያረዝምብሃል ፡ በገንዘብህም ፡ ጠብና ፡
ክርክርን ፡ ይከፍልሃል ፡ ያደክምሃል ፡ ቀጠሮህ
ንም ፡ ያረዝማል ።
እኩሌታውንም ፡ ቢከፍልህ ፡ በጭንቅ ፡ ነው ፡ ፮፤
ዳግመኛም ፡ እሱን ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ወድቆ ፡
ያገኘኸው ፡ ይመስልሃል ፡ ይህስ ፡ ካልሆነ ፡ ገን
ዘብህን ፡ ሁሉ ፡ ታጣለህ ፡ ዳግመኛም ፡ ጠላት ፡
ይሆንሃል ፡ ስድብን ፡ ይሰድብሃል ፡ እርግማን
ንም ፡ ይረግምሃል ፡ ሲያከብርህም ፡ ያዋርድ
ሃል ።
ገንዘባቸውን ፡ እንዳያጡ ፡ ከሰውም ፡ እንዳይ ፯፤
ጣሉ ፡ በመፍራትና ፡ ጠብን ፡ ባለመውደድ ፡
ገንዘባቸውን ፡ የማያበድሩ ፡ ሰዎች ፡ ብዙ ፡
ናቸው ።
ድሀውን ፡ ግን ፡ ታገሠው ፡ ምጽዋቱንም ፡ ፰፤
ስጠው ፡ አልፈኸው ፡ አትሂድ ።
የምጽዋትን ፡ ነገር ፡ የሚናገር ፡ አንቀጽ ፡ ይህ ፡ ፱፤
ነው ፡ ችጋረኛ ፡ ነውና ፡ ድሀውን ፡ በምጽዋት ፡
ተቀበለው ፡ በዶውንም ፡ አትመልሰው ።
ባልንጀራህንና ፡ ወዳጅህን ፡ ከታጣ ፡ ወርቅህ ፡ ፲፤
ተቀብሮ ፡ ከዝግ ፡ በድንጋይም ፡ ሥር ፡ ተቀብሮ ፡
ከጠፋ ።
እግዚአብሔር ፡ መጽውት ፡ ብሎ ፡ ስላዘዘህ ፡ ፲፩፤
ወርቅህን ፡ ከተቀበረበት ፡ አውጥተህ ፡ መጽ
ውት ፡ ከወርቅ ፡ ድልብ ፡ ይልቅ ፡ ፈጽሞ ፡ ምጽ
ዋት ፡ ይጠቅምሃል ።
ምጽዋትን ፡ በድሆች ፡ ቤት ፡ አድልባት ፡ እሷ ፡ ፲፪፤
ትሻላለች ፡ ከመከራህም ፡ ሁሉ ፡ አንተን ፡ ማዳን ፡
ትችላለች ።
በጦርም ፡ ቢሆን ፡ በመሣሪያም ፡ ቢሆን ፡ እሷ ፡ ፲፫፤
ቀድማ ፡ ጥንተ ፡ ጠላትህን ፡ ድል ፡ ትነሣልሃለች ።
የለት ፡ ጠላትህንም ፡ ታጠፋልሃለች ።
ደግ ፡ ሰው ፡ ወዳጁን ፡ ይዋሰዋል ፡ የማያፍር ፡ ፲፬፤
ሰው ፡ ግን ፡ ባልንጀራውን ፡ ቸል ፡ ይላል ።
ስላንተ ፡ ፊንታ ፡ ሰውነቱን ፡ አሳልፎ ፡ ሰጥቷ ፲፭፤
ልና ፡ የተዋሰህን ፡ ሰው ፡ ዋጋውን ፡ አትንካበት ።
ጠብን ፡ ለማጥፋት ፡ መዋስ ፡ ደግ ፡ ነገር ፡ ነው ። ፲፮፤
ኃጢአተኛ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ የዳነውን ፡ ሰው ፡ ዋጋ ፡ ፲፯፤
ይዘነጋል ።
መዋስ ፡ ብዙ ፡ ሰዎችን ፡ አሳዘነ ፡ እንደ ፡ ማዕበ ፲፰፤
ልም ፡ አወካቸው ፡ አርበኞች ፡ ሰዎችንም ፡ አሳ

ታቸው ፡ ልዩ ፡ ወደ ፡ ሆኑ ፡ አሕዛብም ፡ አገር ፡
እንዲሰደዱ ፡ አደረጋቸው ።
፲፱ ኃጢአተኛ ፡ ሰው ፡ በመዋስ ፡ ይጠፋል ፡ ለትር
ፍም ፡ የሚሳሳ ፡ ሰው ፡ በመከራ ፡ ይወድቃል ።
፳ የተቻለህን ፡ ያህል ፡ ባልንጀራህን ፡ ተቀበል ፡
ነገር ፡ ግን ፡ እንዳያስትህ ፡ ራስህን ፡ ጠብቅ ።
፳፩ የኑሮህ ፡ መጀመሪያ ፡ የምትበላው ፡ እህል ፡ የም
ትጠጣው ፡ ውኃ ፡ የምትለብሰው ፡ ልብስ ፡ ነው ፡
ቤትህ ፡ ግን ፡ እፍረትህን ፡ የምትሰውርበት ፡
ነው ።
፳፪ በሌላ ፡ ሰው ፡ ገንዘብ ፡ ለባዕድ ፡ ቤት ፡ ስትዘ
ጋጅ ፡ ደስ ፡ ሲልህ ፡ በቤትህ ፡ ምሰሶ ፡ ሥር ፡ ብት
ቸገር ፡ ይሻልሃል ።
፳፫ ለታናሹም ፡ ለታላቁም ፡ በጎ ፡ ሥራን ፡ ሥራ ፡
በጎ ፡ ነገርንም ፡ ተናገር ።
፳፬ ለመቅላወጥ ፡ ከንዱ ፡ ቤት ፡ ወዳንዱ ፡ ቤት ፡
የሚሄድ ፡ ሰው ፡ እነዋወሩ ፡ ክፉ ፡ ነው ፡ ባደር
ህበትም ፡ በታ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ እንዳትናገር ፡ እወቅ ።
፳፭ ይኸስ ፡ ካልሆነ ፡ ትበላለህ ፡ ትጠጣለህ ፡ ምስጋና ፡
የለህም ፡ ከዚህም ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡
ይመልሱልሃል ።
፳፮ በገንዘብ ፡ በተዘጋጀህ ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ እማቾችን ፡
ገብተህ ፡ ማዕድን ፡ ሥራ ፡ ያለህንም ፡ አብላን ፡
ይሉሃል ።
፳፯ ብትቸገር ፡ ግን ፡ ቤተ ፡ ሰባችን ፡ ውጣ ፡ አማቻ
ችን ፡ ደረሰ ። ቤታችንን ፡ እንወዳለን ፡ ይሉሃል ።
፳፰ ይህ ፡ ነገር ፡ በዋቂ ፡ ሰው ፡ ዘንድ ፡ ጭንቅ ፡ ነው ፡
ያሳደርከው ፡ ሰው ፡ ያዋርድሃል ፡ ያበደርከውም ፡
ሰው ፡ ይሰድብሃል ።

## ምዕራፍ ፡ ፴ ።

፩ የውሉዱን ፡ ነገር ፡ የሚናገር ፡ አንቀጽ ፡ ይህ ፡
ነው ። ልጁን ፡ የሚወድ ፡ ሰው ፡ በሱ ፡ ደስ ፡
ይለው ፡ ዘንድ ፡ ልጁን ፡ መቅጣትን ፡ ቸል ፡ አይ
ልም ።
፪ ልጁን ፡ ያስተማረ ፡ ሰው ፡ በልጁ ፡ መናገር ፡
ያመሰግኑታል ፡ በወዳጁም ፡ ዘንድ ፡ መመኪያ ፡
ይሆነዋል ።
፫ ልጁን ፡ ያስተማረ ፡ ሰው ፡ ጠላቱን ፡ ያስቀናዋል ፡
በወዳጆቹም ፡ ዘንድ ፡ በልጁ ፡ መማር ፡ ደስ ፡
ይለዋል ።
፬ ከሱ ፡ በኋላ ፡ እንደሱ ፡ ያለ ፡ ልጅ ፡ ተክቷልና ፡
አባቱም ፡ ቢሞት ፡ እንዳልሞተ ፡ ይሆናል ።
፭ ለጠላቶቹ ፡ የሚመክት ፡ ለወዳጆቹ ፡ የሚፈተ
ፍት ፡ ከሱ ፡ በኋላ ፡ እንደሱ ፡ ያለ ፡ ልጅ ፡ ተክ
ቷልና ።
፮ በሕይወቱም ፡ ሳለ ፡ በልጁ ፡ ደስ ፡ ብሎታልና ፡
ቢሞትም ፡ ልቡ ፡ አያዝንም ።
፯ ከልቅሷቸው ፡ የተነሣ ፡ ሰውነትህ ፡ ይነዋወጣ
ልና ፡ ልጆችህን ፡ ስለ ፡ ማስተማር ፡ ልቡናህን ፡
አሳዝን ።
፰ ያልተገራ ፡ ፈረስ ፡ ገርጋሬ ፡ ይሆናል ፡ ያልተማረ ፡
ልጅም ፡ አውታታ ፡ ሆኖ ፡ ያድጋል ።
፱ ልጅህን ፡ ካቀማጠልከው ፡ ይበረታታብህ ፡ ዘንድ ፡
ወደ ፡ መበርታት ፡ ይመለሳል ፡ ከሱም ፡ ጋራ ፡
ብትጫወት ፡ ያሳዝንህ ፡ ዘንድ ፡ ወደማሳዘን ፡
ይመለሳል ።
እንዳያሳዝንህም ፡ አትሳቅለት ፡ በፍጻሜ ፡ ዘመ ፲
ንህም ፡ ጥርስህን ፡ ያረግፍሃል ።
በጕልማስነቱ ፡ ሳለ ፡ ልጅህን ፡ አትቅጣው ። ፲፩
ባደገ ፡ ጊዜ ፡ እንዳይከዳህ ፡ በልጅነቱ ፡ ጐን ፡ ፲፪
ጐኑን ፡ ግጠበው ።
በሱ ፡ ጥፋት ፡ አንተ ፡ እንዳታፍር ፡ ልጅህን ፡ ፲፫
አስተምረው ፡ ያገለግልሃል ።
ሰውነቱ ፡ ከታመመ ፡ ሆዱ ፡ ከታሠረ ፡ ባለጸጋ ፡ ፲፬
ሰውነቱ ፡ ጤነኛ ፡ የሆነ ፡ ሆዱ ፡ የተከፈተ ፡ ድሀ ፡
ይሻላል ።
ሰውነትህ ፡ ጤነኛ ፡ ይሁን ፡ ሆድህም ፡ የተከፈተ ፡ ፲፭
ይሁን ፡ ከገንዘብና ፡ ከባለጸግነት ፡ ሁሉ ፡ ይህ ፡
ሰውነቱ ፡ ጤነኛ ፡ የሆነ ፡ ድሀ ፡ ይሻላል ።
በጤና ፡ ከመኖር ፡ ባለጸግነት ፡ አይወደድም ፡ ፲፮
ከልቡና ፡ ተድላ ፡ ደስታም ፡ የሚሻል ፡ ሌላ ፡
ተድላ ፡ ደስታ ፡ የለም ።
ከማያልፍ ፡ ችጋር ፡ ከቍርጥማትም ፡ በሽታ ፡ ፲፯
ሞት ፡ ይሻላል ።
በተዘጋ ፡ አፍ ፡ ፊት ፡ የቀረበ ፡ መብል ፡ ደስ ፡ ፲፰
እንዳያሰኝ ፡ እንደዚሁ ፡ ወደ ፡ መቃብርም ፡ እህ
ልን ፡ የሚወስድ ፡ ሰው ፡ ደስ ፡ አያሰኝም ።
እነሳቸው ፡ አይበሉ ፡ አይጠጡ ፡ አያሸቱ ፡ ለጣ ፲፱
ዖቶች ፡ መሥዋዕት ፡ መሠዋት ፡ ምን ፡ ይጠ
ቅማል ፡ እግዚአብሔርም ፡ በደዌ ፡ የቀሠፈው ፡
ሰው ፡ እንደዚሁ ፡ ነው ።
ጃንደረባ ፡ ቆንጆይቱን ፡ በቀፋት ፡ ጊዜ ፡ እንዲ ፳
ያዝን ፡ በይኖቹ ፡ እያየ ፡ ያዝናል ።
ልቡናህን ፡ የብስጭት ፡ ኀዘን ፡ አታሳዝን ፡ ሰው ፳፩
ነትህንም ፡ አታበሳጭ ።
የልቡና ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ለሰው ፡ ሕይወቱ ፡ ፳፪
ነው ፡ የልቡና ፡ ተድላ ፡ ደስታም ፡ ዘመንን ፡
ያበዛል ።
ሰውነትህን ፡ አለዝብት ፡ የብስጭት ፡ ኀዘን ፡ ፳፫
ብዙ ፡ ሰዎችን ፡ አጥፍቷቸዋልና ፡ የብስጭት ፡
ኀዘን ፡ የምትጠቅመውም ፡ የለምና ፡ የብስጭት ፡
ኀዘንን ፡ ከንተ ፡ ታርቅ ፡ ዘንድ ፡ ልቡናህንም ፡
አረጋጋት ።
ቍጣና ፡ ቅናት ፡ በሕይወት ፡ የሚኖርበትን ፡ ፳፬
ዘመን ፡ ያሳንሳሉ ፡ የብስጭት ፡ ኀዘንም ፡ ጊዜው ፡
ሳይደርስ ፡ ያስረጃል ።
አጫጅን ፡ እየተከተለ ፡ የሚቃርም ፡ ሰው ፡ ማታ ፡ ፳፭
በራት ፡ እንዲተካከል ፡ እኔም ፡ ከነቢያት ፡ በኋላ ፡
ተነሥቼ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ረድኤት ፡ ከነቢያት ፡
ማዕርግ ፡ ደረስኩ ።
ይራቀቁ ፡ ዘንድ ፡ ለሚወዱ ፡ ሰዎችም ፡ ሁሉ ፡ ፳፮
ነው ፡ እንጂ ፡ የደከምኩ ፡ ለኔ ፡ ብቻ ፡ እንዳይ
ደለ ፡ እነሆ ፡ አስተውሉ ።
በሕዝቡ ፡ ላይ ፡ የተሾማችሁ ፡ መኳንንት ፡ ፳፯
ስሙኝ ፡ የአሕዛብም ፡ አለቆች ፡ አድምጡኝ ።
ሚስትህና ፡ ልጅህን ፡ ወዳጅህና ፡ ወንድምህ ፳፰
ንም ፡ አንተ ፡ በሕይወት ፡ ሳለህ ፡ በገንዘብህ ፡

አታሠልጥናቸው ፡ ኋላ ፡ እንዳትጸጸት ፡ በቤት
ህም ፡ ባዕድ ፡ ሰው ፡ አትሹም ፡ ትለምናቸው ፡
ዘንድ ፡ ወደ ፡ መለመን ፡ እንዳትመለስ ፡ በሕይ
ወት ፡ ሳለህ ፡ በገንዘብህ ፡ ላይ ፡ አታሠልጥና
ቸው ።
፳፱ አንተ ፡ በሕይወት ፡ ሳለህ ፡ አእምሮህም ፡ ሳለች ፡
ግብርህን ፡ አትለውጥ ።
፴ አንተ ፡ የልጆችህን ፡ እጅ ፡ ደጅ ፡ ከትጠና ፡
ልጆችህ ፡ አንተን ፡ ቢለምኑህ ፡ ይሻልሃል ።
፴፩ በሥራኸው ፡ ሥራ ፡ አዋቂ ፡ ሁን ፡ በሾሙህም ፡
ቦታ ፡ ሁሉ ፡ ራስህን ፡ አታዋርድ ።
፴፪ በሕይወት ፡ የኖርህበት ፡ ዘመንህ ፡ ሁሉ ፡ በለቀ ፡
ጊዜ ፡ የምትሞትበትም ፡ ቀን ፡ በደረሰች ፡ ጊዜ ፡
የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ገንዘብህን ፡ አውርስ ።
፴፫ አህያህን ፡ ገለባ ፡ አብላው ፡ ሚኒነው ፡ በለንጋ ፡
በኮርቻ ፡ ግረፈው ፡ ባሪያህንም ፡ ቅጣው ፡ መግ
በው ፡ ግዛው ።
፴፬ ባሮችህን ፡ ግዛቸው ፡ ዕረፍት ፡ ታገኛለህ ፡ ብታ
ቦዝናቸው ፡ ግን ፡ ይከራከሩህ ፡ ዘንድ ፡ ከንተም ፡
ነፃ ፡ ይወጡ ፡ ዘንድ ፡ ይወዳሉ ።
፴፭ ቀንበር ፡ መጫን ፡ አንገትን ፡ ዝቅ ፡ ያደርገዋል ፡
ክፉ ፡ ባሪያንም ፡ አለንጋ ፡ እግር ፡ ብረት ፡ ያለ
ዝበዋል ።
፴፮ ባሪያህን ፡ ግዛው ፡ ቦዘን ፡ ብዙ ፡ ክፋትን ፡ ታስ
ተምራለችና ።
፴፯ አበገነህም ፡ አታኑረው ።
፴፰ የሚችለውን ፡ ያህል ፡ ሥራውን ፡ ስጠው ፡ ባይ
ገዛ ፡ ግን ፡ እግር ፡ ብረቱን ፡ አጽናበት ፡ ያለምክር ፡
የምትሠራው ፡ ሥራ ፡ አይኑር ፡ ነገር ፡ ግን ፡
ሥጋዊን ፡ ደማዊን ፡ ሁሉ ፡ አትመነው ።
፴፱ ደግ ፡ ቤተ ፡ ሰብእ ፡ ቢኖርህ ፡ እንደ ፡ ወንድምህ ፡
አድርገው ፡ እንደ ፡ ሰውነትህም ፡ ውደደው ።
፵ ክፉ ፡ ነገር ፡ ብታደርግበት ፡ ግን ፡ ይኮበልልብ
ሃል ፡ ያመልጥሃል ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በየት ፡ ጎዳና ፡
ታገኘዋለህ ።

ምዕራፍ ፡ ፴፩ ።

፩ ሰነፍ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ አሰተኛ ፡ ሕልምን ፡ በከ
ንቱ ፡ ተስፋ ፡ ያደርጋታል ፡ አሰተኛ ፡ ሕልምም ፡
ሰነፍ ፡ ሰውን ፡ ያስደነግጠዋል ።
፪ አሰተኛ ፡ ሕልምን ፡ የሚያምን ፡ ሰው ፡ ጥላን ፡
እንደሚጨብጥ ፡ ነፋስንም ፡ እንደሚከተል ፡
ሰው ፡ ነው ።
፫ ሕልም ፡ ከመሆን ፡ ወዳለመሆን ፡ ይሄዳል ፡ በየ
ምሳሌውም ፡ እየራሱ ፡ ያሳይሃል ።
፬ ካህያ ፡ ምንም ፡ ምን ፡ መሥዋዕት ፡ የሚሆን ፡
በግ ፡ አይወለድም ፡ ከሐሰተኛ ፡ ሕልምስ ፡ እው
ነተኛ ፡ ነገር ፡ በየት ፡ ይገኛል ።
፭ ሐሰተኛ ፡ ሕልም ፡ ጥንቆላ ፡ ሟርት ፡ ሁሉም ፡
ከንቱ ፡ ናቸው ፡ ልቡናንም ፡ ያስደነግጣሉ ፡
እንደ ፡ ምጥም ፡ ያገሙብጣሉ ።
፮ ሐሰተኛ ፡ ሕልም ፡ ብዙ ፡ ሰዎችን ፡ አስቷቸዋ
ልና ፡ እሱንም ፡ ተስፋ ፡ እያደረጉ ፡ ጠፍተዋ
ልና ።
፯ ይቅር ፡ ይል ፡ ዘንድ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ የተገኘ ፡
ካልሆነ ፡ አሰተኛ ፡ ሕልምን ፡ በልብህ ፡ አታኑ
ረው ።
፰ ያለ ፡ ሐሰትስ ፡ ከታየ ፡ በውነት ፡ ይደርሳል ፡
እውነተኛ ፡ ሕልምም ፡ የተረዳ ፡ ይሆናል ።
፱ የተማረ ፡ በመከራ ፡ የተገሠጸ ፡ ሰው ፡ ብዙ ፡ ምሥ
ጢር ፡ ያውቃል ፡ መከራን ፡ የተቀበለ ፡ ሰውም ፡
ጥበብን ፡ ያስተምራል ።
፲ በትምህርት ፡ ያልተነከ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ የሚያው
ቀው ፡ ነገር ፡ የለም ።
፲፩ ብዙ ፡ መከራ ፡ የተቀበለ ፡ ሰው ፡ ብዙ ፡ ትምህ
ርት ፡ ይማራል ።
፲፪ መከራ ፡ በተቀበልኩ ፡ ጊዜ ፡ ብዙ ፡ ምሥጢር ፡
አየሁ ፡ አስቤ ፡ ከተውሁትም ፡ የተናገርሁት ፡
ነገር ፡ በዛ ።
፲፫ ለሞት ፡ እስከደርስ ፡ ድረስ ፡ ሁልጊዜ ፡ መከራ ፡
ተቀብያለሁና ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ እግዚአብሔር ፡
ከመከራ ፡ ያድነኛል ።
፲፬ እግዚአብሔርን ፡ የምትፈራ ፡ ሰውነት ፡ ከመከ
ራው ፡ ትድናለች ።
፲፭ እሱን ፡ ያመኑ ፡ ሁሉ ፡ ይድናሉ ።
፲፮ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈራ ፡ ሰውን ፡ የሚያስፈ
ራው ፡ የለም ፡ እሱ ፡ አለኝታው ፡ ነውና ፡ መከራ ፡
መጥቶበት ፡ አይደነግጥም ።
፲፯ እሱ ፡ ያድርበታልና ፡ የታመነ ፡ ወዳጁም ፡
ነውና ።
፲፰ እግዚአብሔርን ፡ የምትፈራ ፡ ሰውነት ፡ የተደነ
ቀች ፡ ናት ።
፲፱ ኃይልነቱ ፡ የታመነ ፡ ነውና ፡ ረድኤቱም ፡ ጽኑ ፡
ነውና ፡ የእግዚአብሔር ፡ ዓይኖቹ ፡ የሚፈሩ
ትን ፡ ሰዎች ፡ ይመለከታሉ ፡ በረሀውን ፡ ያቀዘ
ቅዝልሃል ፡ ከቀትር ፡ ፀሐይም ፡ ይሠውርሃል ፡
ከመከራ ፡ ይጠብቅሃል ፡ ረድቶም ፡ ከመከራ ፡
ያድንሃል ።
፳ ሰውነትህን ፡ ያገናታል ፡ ዓይኖችህንም ፡ ያበራ
ቸዋል ፡ ከደዌ ፡ ይፈውሳል ፡ ደኅንነትንም ፡ ይሰ
ጣል ፡ በረከትንም ፡ ይሰጣል ።
፳፩ የበደል ፡ መሥዋዕት ፡ የተጠላ ፡ ነው ፡ የኃጢአ
ተኞችም ፡ ቍርባናቸው ፡ አደፈኛ ፡ ነው ።
፳፪ ሕግ ፡ የዘነጉ ፡ ሰዎች ፡ መሥዋዕትን ፡ አይቀበ
ልም ።
፳፫ በመብህ ፡ ብዛት ፡ ኃጢአትህን ፡ የሚያስተሠር
ይልህ ፡ አይደለም ።
፳፬ ልጁን ፡ በባቱ ፡ ፊት ፡ የሚገድለው ፡ ሰው ፡ ደስ ፡
እንዳያሰኝ ፡ ሰርቆ ፡ ቀምቶ ፡ መባ ፡ የሚያገባ ፡
ሰው ፡ እንደዚያ ፡ ደስ ፡ አያሰኝም ።
፳፭ የድሀ ፡ ሕይወቱ ፡ ምጽዋት ፡ መለመን ፡ ነው ፡
እምቢ ፡ ያለው ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ነፍሰ ፡ ገዳይ ፡ ነው ።
፳፮ ባልንጀራውን ፡ የገደለ ፡ ሰው ፡ ደስ ፡ እንዳያ
ሰኝ ፡ ነገር ፡ ሠርቶ ፡ ባልና ፡ ሚስትንም ፡ የሚያ
ፋታ ፡ ሰው ፡ ባልንጀራውን ፡ እንደ ፡ ገደለ ፡
ሰው ፡ ነው ።
፳፯ የምንደኛውን ፡ ደመወዝ ፡ የቀማ ፡ ሰው ፡ ደሙን ፡
ማፍሰሱ ፡ ነው ።

፳፰ አንዱ ፡ ሲሠራ ፡ አንዱ ፡ ቢያፈርስ ፡ የሁለቱስ ፡
ድካማቸው ፡ ምን ፡ ይጠቅማል ።
፳፱ አንዱ ፡ ቢመርቅ ፡ አንዱ ፡ ቢረግም ፡ ከሁለቱ ፡
የማናቸውን ፡ ቃል ፡ ይሰማል ።
፴ ሬሳ ፡ ከዳሰሰ ፡ በኋላ ፡ እጁን ፡ ቢታጠብ ፡ ዳግ
መኛ ፡ ሬሳውን ፡ ከዳሰሰ ፡ የፊተኛው ፡ መታ
ጠብ ፡ ምን ፡ ይጠቅመዋል ።
፴፩ ስለ ፡ ኃጢአቱ ፡ የሚጾም ፡ ሰው ፡ ዳግመኛ ፡ ይበ
ድል ፡ ዘንድ ፡ ቢሄድ ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ጸሎቱን ፡
ማን ፡ ይሰማዋል ፡ ሰውነቱንስ ፡ ማሳዘን ፡ ምን ፡
ይጠቅመዋል ።

ምዕራፍ ፡ ፴፪ ።

፩ ሕጉን ፡ የሚጠብቅ ፡ ሰው ፡ መባ ፡ ያገባል ።
፪ ትእዛዙን ፡ የሚሰማ ፡ ሰው ፡ ድኅነቱ ፡ ሊደረግ
ለት ፡ መሥዋዕት ፡ ይሠዋል ።
፫ ስንዴ ፡ የሚያገባ ፡ ሰው ፡ ዋጋውን ፡ ይመልሳል ።
፬ ምጽዋት ፡ የመጸወተ ፡ ሰው ፡ የምስጋና ፡ መሥ
ዋዕትን ፡ ሠዋ ።
፭ የእግዚአብሔር ፡ ፈቃዱ ፡ ኃጢአት ፡ እንዳት
ሠራ ፡ ነው ፡ ከበደልም ፡ ትርቅ ፡ ዘንድ ፡ ፈቃዱ ፡
ነው ።
፮ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክር
ስቲያን ፡ ባዶህን ፡ አትግባ ።
፯ ይህን ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ ትእዛዙ ፡ አድርግ ።
፰ የደግ ፡ ሰው ፡ መሥዋዕት ፡ እግዚአብሔርን ፡
ደስ ፡ ያሰኘዋል ፡ መዓዛውም ፡ ወደ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ይደርሳል ።
፱ የደግ ፡ ሰው ፡ መሥዋዕት ፡ የከበረ ፡ ነው ፡ ስም ፡
አጠራሩም ፡ ሁሉ ፡ አይዘነጋበትም ።
፲ ፊትህን ፡ ደስ ፡ እያለህ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመ
ስግነው ፡ ከመጀመሪያ ፡ እኽመራህም ፡ አሥራት ፡
ማግባትን ፡ አትተው ።
፲፩ የሰጠህን ፡ ገንዘብ ፡ ሁሉ ፡ ፊትህን ፡ ደስ ፡ እያ
ለህ ፡ ስጠው ፡ ደስ ፡ እያለህም ፡ ያኽመራህን ፡
አሥራት ፡ አግባ ።
፲፪ እንደ ፡ ክብሩ ፡ ብዛት ፡ መጠን ፡ ለእግዚአብሔር ፡
መባህን ፡ አግባ ፡ በጅህ ፡ ካገኘኸው ፡ ገንዘብም ፡
ፊትህን ፡ ደስ ፡ እያለው ፡ አግባለት ።
፲፫ እግዚአብሔር ፡ ዋጋህን ፡ ይመልስልሃልና ።
ሰባት ፡ እጥፍም ፡ አድርጎ ፡ ይሰጥሃልና ፡ ፊት
ህን ፡ ደስ ፡ እያለህ ፡ አግባለት ።
፲፬ አይቀበልልህምና ፡ ማማለጃን ፡ አታግባለት ።
፲፭ እግዚአብሔር ፡ የውነት ፡ ዳኛ ፡ ነውና ፡ ፊትን ፡
አይቶም ፡ አያደላምና ፡ የበደልን ፡ መሥዋዕት ፡
የሚቀበል ፡ አይምሰልህ ።
፲፮ ደሀውንም ፡ ስለ ፡ ችጋሩ ፡ ከባለጸጋው ፡ አይለየ
ውም ፡ የተበደለ ፡ ሰውንም ፡ ጩኸት ፡ ይሰማል ።
፲፯ እናት ፡ አባት ፡ የሞቱበት ፡ ልጅ ፡ ልመናን ፡ ቸል ፡
አይልም ፡ ባልቴት ፡ ሴትንም ፡ ያስለቀሳት ፡ ሰው ፡
ቢኖር ።
፲፰ እንባንም ፡ በፊቷ ፡ ላይ ፡ ብታወርድ ።
፲፱ እንደዚሁ ፡ ባስለቀሳት ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ እንባ ፡ ይወ
ርዳል ።

በውነት ፡ የሚያገለግለውን ፡ ሰው ፡ ልመናውን ፡ ፳
ይቀበለዋል ፡ ልመናውም ፡ ወደ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ትደርሳለች ።
የድሀውም ፡ ልመና ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፳፩
ትደርሳለች ፡ ወደሱ ፡ እስክትደርስ ፡ ደርሳ ፡ አት
መለስም ፡ እግዚአብሔርም ፡ እስኪያያት ፡ ድረስ ፡
ደርሳ ፡ አትመለስም ።
ለደጋግ ፡ ሰዎች ፡ ይፈርድላቸዋል ፡ ጠላታቸው ፳፪
ንም ፡ ተበቅሎ ፡ ያጠፋላቸዋል ፡ የጠላታቸውን ፡
ሥልጣን ፡ እስኪያጠፋ ፡ ድረስ ፡ ስለነሳቸው ።
ፈጽሞ ፡ ቸል ፡ አይልም ።
አሕዛብን ፡ ተበቅሎ ፡ ያጠፋቸዋል ፡ በደለኞች ፳፫
ንም ፡ ሁሉ ፡ ያጠፋቸዋል ፡ የኃጢአተኞችንም ፡
ሥልጣን ፡ ያጠፉታል ።
ለሰው ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ሥራው ፡ ዋጋውን ፡ ይከ ፳፬
ፍለዋል ፡ የወገኖቹን ፡ በቀል ፡ ይመልሳልና ፡
በቸርነቱም ፡ ደስ ፡ ያሰኛቸዋልና ።
ስለ ፡ ሰዎችም ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ሥራቸው ፡ እንደ ፡ ፳፭
ሥራቸው ፡ ፍዳውን ፡ ይከፍላቸዋል ።
ዝናም ፡ የያዘ ፡ ደመና ፡ በበረሃ ፡ ደስ ፡ እንዲያ ፳፮
ሰኝ ፡ በመከራው ፡ ጊዜ ፡ ይቅርታን ፡ የሚያገኝ ፡
ሰው ፡ የተደነቀ ፡ ነው ።

ምዕራፍ ፡ ፴፫ ።

የፍጹም ፡ ኃይል ፡ ፈጣሪ ፡ አቤቱ ፡ ይቅር ፡ ፩
ብለህ ፡ ከመዓት ፡ ወደ ፡ ምሕረት ፡ ተመለስልን ።
በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ አንተን ፡ መፍራት ፡ አሳድር ። ፪
ልዩ ፡ በሆኑ ፡ ወገኖችም ፡ ሥልጣንህን ፡ ግለጥ ፡ ፫
ኃይልህንም ፡ ይዩ ።
እነሳቸው ፡ የኛን ፡ ጥፋት ፡ ሲያዩ ፡ በኛ ፡ ጥፋት ፡ ፬
እንደተመሰገንህ ፡ እንደዚሁም ፡ ሁሉ ፡ እኛ ፡
የነሳቸውን ፡ ጥፋት ፡ ስናይ ፡ በነሳቸው ፡ ጥፋት ፡
ተመስገን ።
አቤቱ ፡ ያላንተ ፡ ሌላ ፡ ፈጣሪ ፡ የለምና ፡ እኛ ፡ ፭
እንዳወቅንህ ፡ እነሱም ፡ ይወቁህ ።
ታምራትህን ፡ አሳይ ፡ ጌትነትህንም ፡ ግለጥ ። ፮
በሥልጣንህ ፡ ኃይል ፡ በከበረ ፡ ሥልጣንህም ። ፯
ጥፋትን ፡ አምጣባቸው ፡ መቅሠፍትንም ፡ አምጣ ። ፰
በደለኞችን ፡ አጥፋቸው ፡ አንጥያኮስንም ፡ አጥ ፱
ፋቸው ።
የባሮችህን ፡ መሐላ ፡ አስብ ፡ የሚጠፉባትንም ፡ ፲
ቀን ፡ ፈጥነህ ፡ አድርጋት ።
በእሳት ፡ አጥፋቸው ፡ ከነሳቸው ፡ ያመለጡት ፲፩
ንም ፡ በጦር ፡ አጥፋቸው ፡ በወገኖችህም ፡ ክፉ ፡
ያደረጉ ፡ ሰዎችን ፡ ሞት ፡ ያግኛቸው ።
ያለኛ ፡ ሌላ ፡ ሰው ፡ የለም ፡ የሚሉ ፡ የጠላቶችን ፡ ፲፪
አለቆችን ፡ ሥልጣን ፡ አጥፋ ።
የያዕቆብን ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ሰብስባቸው ። ፲፫

ምዕራፍ ፡ ፴፬ ።

የሚጣፍጥ ፡ እህልን ፡ በጎ ፡ ልቡናህን ፡ አይን ፩
ቁትም ፡ ለባለጸግነት ፡ መትጋት ፡ ፈጽሞ ፡ ሰው
ነት ፡ ያከሳል ፡ ገንዘብህንም ፡ ማሰብ ፡ እንቅልፍ ፡
ያሳጣል ።

፩፤ የሚጠራጠሩት ፡ ጠላት ፡ መኖርም ፡ በንጉልቻ ፡
እንቅልፍ ፡ ያስረሳል ፡ ጽኑ ፡ ቍርጥማት ፡ ያተ
ጋል ፡ እንቅልፍም ፡ ያሳጣል ።
፪፤ በለጸጋ ፡ ገንዘብ ፡ ያደልብ ፡ ዘንድ ፡ ይዘራል ፡
ያረፈም ፡ ጊዜ ፡ በጥጋብ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ።
፫፤ ድሀ ፡ ገንዘብ ፡ በማጣት ፡ ይደክማል ፡ በረፈም ፡
ጊዜ ፡ ወደ ፡ ልመና ፡ ይመለሳል ።
፬፤ ገንዘብ ፡ የሚወድ ፡ ሰው ፡ አይጸድቅም ፡ ኃጢ
አትንም ፡ የሚወዳት ፡ ሰው ፡ ይከተላታል ።
፭፤ ገንዘብ ፡ ወደው ፡ የጠፉ ፡ ሰዎች ፡ ብዙ ፡ ናቸው ፡
ሞታቸውንም ፡ በፊታቸው ፡ አይዋት ።
፮፤ ገንዘብ ፡ ለሚፈልጓት ፡ ሰዎች ፡ እንቅፋት ፡ ናት ፡
ሰነፍ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በሷ ፡ ይሰነካከላል ።
፯፤ ከኃጢአት ፡ ንጹሕ ፡ የሆነ ፡ ባለጸጋ ፡ ልቡናው
ንም ፡ ወደ ፡ ገንዘብ ፡ ያልወሰደ ፡ ባለጸጋ ፡ የተ
ደነቀ ፡ ነው ።
፰፤ ለወገኖቹ ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ ያደረገ ፡ ማነው ፡ እንጃ ፡
እናድንቀው ።
፱፤ በገንዘቡ ፡ ያወቀበት ፡ ከሕግም ፡ ወጥቶ ፡ ያል
ሳተ ፡ ሰው ፡ ማነው ፡ እንጃ ፡ እናድንቀው ፡
እሱም ፡ መመኪያ ፡ የሆነው ፡ ኃጢአት ፡ መሥ
ራት ፡ ሲቻለው ፡ ኃጢአት ፡ የማይሠራ ፡ ማነው ።
፲፤ ክፉ ፡ መሥራት ፡ ሲቻለው ፡ ክፉ ፡ የማያደ
ርግ ፡ ሰው ፡ ማነው ፡ እንጃ ፡ እናድንቀው ፡ በረ
ከቱ ፡ ትጸናለች ፡ ምጽዋቱም ፡ በአሕዘብ ፡ አገር ፡
ትሰማ ።
፲፩፤ በታላቅ ፡ ማዕድም ፡ ብትቀመጥ ፡ ለመብላት ፡
ጕሮሮህን ፡ አትክፈት ፡ (ሁሉን ፡ ውጬው ፡
አትበል ፡) በውስጡም ፡ ብዙ ፡ ሥሩ ፡ አትበል ፡
፲፪፤ የሰው ፡ ዓይን ፡ ክፉ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አስብ ፡ ከሰው ፡
ዓይን ፡ የሚከፋ ፡ ምን ፡ አለ ፡ ስለዚህም ፡ ነገር ፡
የሰውን ፡ ዓይን ፡ ታላቅሳለች ።
፲፫፤ ላየኸው ፡ ሁሉ ፡ አትሳሳ ፡ እጅህን ፡ አትንከር ፡
ድስቱን ፡ ወዳንተ ፡ አትጐትት ፡ ድስቱን ፡ አት
ጥረግ ።
፲፬፤ ባልንጀራህ ፡ ያቀረበልህን ፡ ሁሉ ፡ እወቅ ፡ ያቀ
ረበልህንም ፡ ሁሉ ፡ ተረዳ ።
፲፭፤ ያቀረቡልህን ፡ እንደ ፡ ብልህ ፡ ሰው ፡ ሁነህ ፡ ብላ ፡
ባልንጀራህን ፡ እንዳታስጸይፍ ፡ ስታላምጥ ፡ አፍ
ህን ፡ አታጩህ ።
፲፮፤ ከሰው ፡ ሁሉ ፡ አስቀድመህ ፡ ተው ፡ አትሳሳ ፡
እንደማይጠግብ ፡ ሰውም ፡ አትሁን ።
፲፯፤ በሰው ፡ መካከልም ፡ ብትቀመጥ ፡ እጅህን ፡ አስ
ቀድመህ ፡ አታውርድ ።
፲፰፤ በመኝታህ ፡ ሆድህን ፡ እንዳይከብድህ ፡ ጥቂት ፡
እንደሚበቃው ፡ እንደ ፡ አዋቂ ፡ ሰው ፡ መጥ
ነህ ፡ ብላ ።
፲፱፤ ሰውነቱን ፡ የሚመጥናት ፡ ሰው ፡ እንቅልፍ ፡
ጤና ፡ ነው ፡ ከእንቅልፉም ፡ በጧት ፡ በተቀሰ
ቀሰ ፡ ጊዜ ፡ ሆዱን ፡ አይከብደውም ፡ ለማይጠ
ግብ ፡ ለስሱ ፡ ሰው ፡ በሽታው ፡ ቍንጣን ፡ ጓታ ፡
ብስና ፡ ነው ።
፳፤ ትበላ ፡ ዘንድ ፡ ግድ ፡ ቢሉህ ፡ ቀድመሃቸው ፡
ተነሥ ፡ ከመብላትም ፡ እረፍ ።

ልጄ ፡ አድምጠኝ ፡ ምክሬንም ፡ አትናቅ ፡ ኋላ ፡ ፳፩፤
ነገሬን ፡ ታገኘዋለህ ፡ ምንግን ፡ እንዳታጣ ፡ በሥ
ራኸው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ደካማ ፡ አትሁን ።
ለጋስን ፡ ሰው ፡ በሥራው ፡ ማማር ፡ ይመርቁ ፳፪፤
ታል ፡ ንፉግ ፡ ሰውንም ፡ በክፉ ፡ ሥራው ፡ ይረ
ግሙታል ።
መጠጥ ፡ ብዙ ፡ ሰዎችን ፡ አስቷቸዋልና ፡ ወይን ፡ ፳፫፤
በጠጣህ ፡ ጊዜ ፡ አትታበይ ።
ጽኑ ፡ ብረትን ፡ በወናፍ ፡ ይፈትኑታል ፡ እንደ ፳፬፤
ዚሁም ፡ ሁሉ ፡ የትቢተኞችን ፡ ልቡናቸውን ፡
ወይን ፡ ይፈትነዋል ።
የሰው ፡ ደኅንነቱ ፡ ወይን ፡ መጠጣት ፡ ነው ፡ ፳፭፤
መጥኖ ፡ ለሚጠጣም ፡ ሰው ፡ ተድላ ፡ ደስታው ፡
ነው ፡ እሱ ፡ ለሰው ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ሊሆን ፡
ተፈጥሯልና ፡ ወይን ፡ ለማይጠጣ ፡ ሰው ፡ ደኅ
ንነቱ ፡ ምንድነው ።
ለልቡና ፡ ፈጽሞ ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ነው ፡ ወይ ፳፮፤
ን ፡ መጥኖ ፡ በጊዜው ፡ መጠጣት ፡ ደግ ፡ ነው ።
ወይን ፡ የልቡና ፡ ኀዘንን ፡ ያስረሳል ፡ ለሚያሉ ፳፯፤
ቅስ ፡ ለሚያዝንም ፡ ሰው ፡ ወይን ፡ አጠጣው ።
ሰነፍ ፡ ሰው ፡ ወይን ፡ በጠጣ ፡ ጊዜ ፡ ክርክር ፡ ፳፰፤
ያበዛል ፡ ይስታል ፡ ይበድላል ፡ የመጠጥ ፡ ብዛት ፡
ኃይል ፡ ይሰጣል ፡ ቍስልም ፡ ያሳጣ ።
ወይን ፡ ጠጥቶ ፡ ሳለ ፡ ባልንጀራህን ፡ አትቈ ፳፱፤
ጣው ፡ ልቡናው ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ ሳለ ፡ አታሳዝ
ነው ፡ የምትነቅፈውንም ፡ አትንገረው ፡ እሱ ፡
ሰክሮ ፡ ሳለ ፡ ጕዳይህንም ፡ አትለምነው ።

ምዕራፍ ፡ ፴፪ ።

አለቃም ፡ አድርገው ፡ ቢሾሙህ ፡ ራስህን ፡ ፩፤
አታኵራ ፡ ከነሳቸው ፡ እንዳንዱ ፡ ሁን ፡ አዘናቸ
ውንም ፡ እዘን ፡ ተቀምጠህም ፡ ፍረድላቸው ።
ፍርድህን ፡ ጨርሰህ ፡ እረፍ ፡ መልክትህንም ፡ ፪፤
ጨርሰህ ፡ የክብር ፡ ዘውድን ፡ ታገኝ ፡ ዘንድ ፡
ከሳቸው ፡ ጋራ ፡ ደስ ፡ ይበልህ ።
ሽማግሌ ፡ ይገባሃል ፡ ተናገር ፡ ለበጎ ፡ ነገር ፡ ቻል ፡ ፫፤
አትበል ፡ የጥበብህንም ፡ ነገር ፡ ተናገር ።
ለመረመረህ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ምሥጢርህን ፡ አት ፬፤
ናገር ፡ እንዳገኘህም ፡ አትራቀቅ ።
በወርቅ ፡ ጌጥ ፡ ያለ ፡ የከበረ ፡ ዕንቍ ፡ ያማረ ፡ ፭፤
የተወደደ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ዘፈንም ፡ ወይን ፡ በሚ
ጠጡ ፡ ሰዎች ፡ ዘንድ ፡ እንደዚሁ ፡ ያማረ ፡ የተ
ወደደ ፡ ነው ።
በወርቅ ፡ ዝርግፍ ፡ ያለ ፡ ዕንቍም ፡ ያማረ ፡ እንደ ፡ ፮፤
ሆነ ፡ መሰንቆና ፡ ዘፈንም ፡ እንደሱ ፡ በመጠጥ ፡
ቤት ፡ ያማረ ፡ የተወደደ ፡ ነው ።
ጐልማሳ ፡ ከሰናበቱህ ፡ ተናገር ፡ በጭንቅ ፡ ተና ፯፤
ገር ፡ ዳግመኛም ፡ ቢጠይቁህ ።
አንድ ፡ ጊዜ ፡ ተናግረህ ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ነገር ፰፤
ህን ፡ ጨርስ ፡ እያወቅህም ፡ በንደበትህ ፡ ዝም ፡
በል ።
በመኳንንት ፡ መካከል ፡ አትቀመጥ ፡ ሌላ ፡ ሰው ፡ ፱፤
ሲናገር ፡ ነገርህን ፡ አትናገር ።
በነጐድጓድ ፡ ፊት ፡ የሚሄድ ፡ መብረቅ ፡ እንዲ ፲፤

ያስፈራ ፡ የሚያፍር ፡ ሰው ፡ መወደዱ ፡ በሬቱ ፡ ነው ።

፲፩ ወደ ፡ ቤትህ ፡ ገብተህ ፡ ሁሉን ፡ በጊዜው ፡ ጊዜ ፡ መጥነህ ፡ አድርግ ፡ በዚያም ፡ ደስ ፡ ይበልህ ፡ ተጫወት ።

፲፪ የሚገባውን ፡ የሚወደደውን ፡ ሁሉ ፡ አድርግ ፡ የትዕቢትን ፡ ነገር ፡ እንዳትናገር ፡ እወቅ ፡ በቃልህም ፡ አትበድል ።

፲፫ ከዚህ ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ ፈጣሪህን ፡ አመስግነው ፡ እሱም ፡ ከበረከቱ ፡ ሁሉ ፡ ያጠግብሃል ።

፲፬ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈራ ፡ ሰው ፡ ለሕጉ ፡ ይገዛል ፡ ወደሱም ፡ ፈጥነው ፡ የሚሄዱ ፡ ሰዎች ፡ ፈቃዳቸውን ፡ ያገኛሉ ።

፲፭ ሕጉንም ፡ የሚጠብቀው ፡ ነው ፡ ሕጉን ፡ ከመጠበቁ ፡ የተነሣ ፡ ይጠግባል ፡ የሚጠራጠር ፡ ሰው ፡ ግን ፡ በሱ ፡ ይጠፋል ፡ ይስታል ።

፲፮ ለሚፈሩት ፡ ሰዎች ፡ እግዚአብሔር ፡ ይፈርድላቸዋል ፡ በፍላ ፡ በለጸግነትም ፡ ሳሉ ፡ ጠላታቸውን ፡ ተበቅሎ ፡ ያጠፋላቸዋል ።

፲፯ ኃጢአተኛ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ የሚመክሩትን ፡ ሰዎች ፡ አይሰማም ፡ ሁሉም ፡ እንደ ፡ ልቡ ፡ ይመስለዋል ።

፲፰ ብልህ ፡ ሰው ፡ ያለምክር ፡ የሚሠራው ፡ ሥራ ፡ የለም ፡ የሚሠራውም ፡ ሥራ ፡ ያበጀ ፡ ይሆንለታል ፡ የሚያገዝን ፡ ጠላት ፡ ትቢተኛ ፡ ያለምክር ፡ ሥራውን ፡ ሠርቶ ፡ ፍርሃትን ፡ ያደርጋል ።

፲፱ ልጄ ፡ አንተ ፡ ግን ፡ ያለምክር ፡ የምትሠራው ፡ ሥራ ፡ የለም ፡ የሠራኸውንም ፡ ሥራ ፡ አታጥፋ ።

፳ በጥፋት ፡ ድንጋይ ፡ እንዳትሰነከል ፡ ፊጽመህ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ አትሒድ ።

፳፩ ጠላትህን ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ አትመነው ።

፳፪ በፈቃድህ ፡ ጸንቶ ፡ የሚኖር ፡ ልጅህን ፡ ስንኳ ፡ አትመነው ።

፳፫ በሠራኸው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ሰውነትህን ፡ ደስ ፡ አሰኛት ፡ በሁሉም ፡ ትእዛዙን ፡ ጠብቅ ።

፳፬ ሕጉን ፡ የሚጠብቅ ፡ ሰው ፡ የመጻፉን ፡ ትእዛዝ ፡ ይሰማል ፡ በእግዚአብሔርም ፡ ያመነ ፡ ሰው ፡ የሚያጣው ፡ ነገር ፡ የለም ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፮ ።

፩ ይፈትኑት ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈራ ፡ ሰውን ፡ መከራ ፡ አያገኘውም ፡ ከመከራዪቱም ፡ ይድናል ።

፪ ብልህ ፡ ሰው ፡ መጽሐፍ ፡ መስማትን ፡ ይወዳል ፡ የሚጠራጠር ፡ በመጽሐፉ ፡ የማያምን ፡ ሰው ፡ ግን ፡ በጥልቅ ፡ ነፋስ ፡ መካከል ፡ እንደምትንገላል ፡ መርከብ ፡ ይሆናል ።

፫ ብልህ ፡ ሰው ፡ አምኖ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ ይገዛል ፡ እግዚአብሔርም ፡ የታመነ ፡ ወዳጁ ፡ ይሆናል ፡ ደስ ፡ ያሰኘዋል ።

፬ የምትነግረውን ፡ ነገርህን ፡ አዘጋጅተህ ፡ አድምጥ ፡ የምታደርገውንም ፡ ምክር ፡ አጽንተህ ፡ ተናገር ።

፭ የሰነፍ ፡ ሰው ፡ ልቡና ፡ እንደ ፡ ሠረገላ ፡ መንኰራኵር ፡ ነው ፡ የፈሪ ፡ ሰው ፡ ምክር ፡ እንደምትሽከረከር ፡ እንዝርት ፡ ነው ።

፮ የተገራ ፡ ፈረስ ፡ እንደ ፡ በጎ ፡ ወዳጅ ፡ ነው ።

፯ በንዱ ፡ ዘመን ፡ የሚመላለሰው ፡ ቀን ፡ ሁሉ ፡ በፀሐይ ፡ ብርሃን ፡ ጸንቶ ፡ ሲኖር ፡ አንዲቱ ፡ ቀን ፡ ከንዲቱ ፡ ቀን ፡ በምን ፡ ተበልጣለች ፡ ቢሉ ።

፰ ቀኑ ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ትእዛዝ ፡ ይለያል ፡ የበዓሉም ፡ ጊዜ ፡ በቍጥሩ ፡ ይታወቃል ።

፱ ከቀኑም ፡ ያከበረው ፡ ያገነነው ፡ አለ ። ከነሳቸውም ፡ በየጊዜያቸውና ፡ በየቍጥራቸው ፡ አዝመራንና ፡ ክረምትን ፡ በጋን ፡ ለየ ።

፲ እኛ ፡ ሁላችን ፡ የአዳም ፡ ልጆች ፡ ከመሬት ፡ ተገኘን ፡ አዳምም ፡ ከመሬት ፡ ተፈጠረ ።

፲፩ እግዚአብሔር ፡ በጥበቡ ፡ ብዛት ፡ ለያቸው ፡ በየሥራቸው ፡ አዘጋጃቸው ።

፲፪ ከነሳቸው ፡ የመረቀው ፡ አለ ፡ ያገነናቸውም ፡ አሉ ፡ ከነሳቸው ፡ የለያቸው ፡ አሉ ፡ የታያቸውም ፡ አሉ ። ከነሳቸው ፡ የረገማቸው ፡ ያጐሳቈላቸውም ፡ አሉ ፡ እንደ ፡ ሥራቸውም ፡ የወነጀላቸውም ፡ አሉ ።

፲፫ እኛ ፡ በሱ ፡ ዘንድ ፡ በሸክላ ፡ ሠሪ ፡ እጅ ፡ እንዳለ ፡ ጭቃ ፡ ነን ፡ ፍጥረቱ ፡ ሁሉ ፡ በሥራቱ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፡ ሰውም ፡ በፈጣሪው ፡ ሥልጣን ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፡ ሁሉንም ፡ እንደ ፡ ሥራው ፡ ይከፈለዋል ።

፲፬ የበጎ ፡ ሥራ ፡ ተቃራኒዋ ፡ ክፋት ፡ ናት ፡ የሞትም ፡ ተቃራኒዋ ፡ ሕይወት ፡ ናት ፡ እንደዚሁም ፡ የጽድቅ ፡ ተቃራኒዋ ፡ ኃጢአት ፡ ናት ።

፲፭ ከዚህ ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ፍጥረቱን ፡ ተመልከት ፡ አንዱም ፡ አንዱም ፡ በየወገኑ ፡ ሁለት ፡ ሁለት ፡ ሁኖ ፡ ተፈጠረ ።

፲፮ እኔ ፡ ግን ፡ ከሁሉ ፡ በኋላ ፡ ተነሥቼ ፡ ይኸን ፡ ነገር ፡ አሰብሁት ፡ ከጥንቱም ፡ ጀምሬ ፡ መረመርኩት ።

፲፯ በስምህ ፡ የተጠሩ ፡ ወገኖችህን ፡ አቤቱ ፡ ይቅር ፡ በል ፡ በበህር ፡ ልጅህ ፡ ያስመሰልኋቸው ፡ እስራኤልንም ፡ ይቅር ፡ በል ።

፲፰ የምትመሰገንበት ፡ ቤተ ፡ መቅደስን ፡ በረድኤት ፡ የምታድርበት ፡ አገርህ ፡ ኢየሩሳሌምንም ፡ ይቅር ፡ በል ።

፲፱ በጽዮንም ፡ የቃልህን ፡ ረድኤት ፡ አሳድርበት ፡ ረድኤትህንም ፡ በወገኖችህ ፡ አሳድር ።

፳ አስቀድሞ ፡ ለፈጠካቸው ፡ ሰዎች ፡ ሕግህን ፡ አስተምራቸው ፡ ለነቢያትም ፡ ስምህን ፡ አጽና ።

፳፩ አገልጋዮችህ ፡ ነቢያትን ፡ ያምኗቸው ፡ ዘንድ ፡ ተስፋ ፡ ላደረጉህ ፡ ለመቃብያን ፡ ዋጋቸውን ፡ ስጣቸው ።

፳፪ አቤቱ ፡ የባሮችህንና ፡ የነቢያትን ፡ ጸሎታቸውን ፡ ስማ ፡ የአሮንንም ፡ በረከት ፡ በወገኖችህ ፡ አሳድር ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ለዘላለሙ ፡ ፈጣሪ ፡ እግዚአብሔር ፡ አንተ ፡ ብቻ ፡ እንደሆንክ ፡ ይወቁ ።

፳፫ እህል ፡ ሁሉ ፡ ይበላል ፡ ወደ ፡ ሆድ ፡ ይወርዳል ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ከህል ፡ የሚጣፍጥ ፡ እህል ፡ አለ ።

፳፬ የእህልን ፡ ጣዕም ፡ ሁሉ ፡ ጕሮሮ ፡ ይለየዋል ፡

እንደዚሁም ፡ ሁሉ ፡ ያዋቂ ፡ ሰው ፡ ልቡና ፡
እሰት ፡ ነገርን ፡ ይለያል ።
፳፭ ከፉ ፡ ልቡና ፡ እሰት ፡ ነገርን ፡ ያስባል ፡ ብዙ ፡
መከራ ፡ የተቀበለ ፡ ሰውም ፡ ትዕግሥትን ፡ ይለ
ምደዋል ።
፳፮ ወንድ ፡ ሁሉ ፡ ሚስት ፡ አገባሁ ፡ ይላል ፡ ነገር ፡
ግን ፡ ከሴት ፡ የምትበልጥ ፡ ሴት ፡ አለች ።
፳፯ የሴት ፡ መልኳ ፡ ፊቷን ፡ ያበራዋል ፡ ከሰው ፡
ሁሉ ፡ ፈቃድ ፡ እሷ ፡ ትበልጣለች ።
፳፰ የዋህ ፡ ብትሆን ፡ ቃሏም ፡ ያማረ ፡ ቢሆን ፡ ባሏ ፡
እንደ ፡ መልአክ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ እንደ ፡ ሰው ፡
አይደለም ።
፳፱ ረዳቱ ፡ ናትና ፡ ጽኑ ፡ መጠጊያውም ፡ ናትና ፡
ልባም ፡ ሴትን ፡ ያገባ ፡ ሰው ፡ ተድላ ፡ ደስታ
ውን ፡ አገኘ ።
፴ ቅጥር ፡ የሌለው ፡ ቤት ፡ ገንዘቡ ፡ እንዲሠረቅ ፡
እንደዚሁ ፡ ሚስትም ፡ የሌለው ፡ ሰው ፡ ተጨ
ንቆ ፡ ይኖራል ።
፴፩ ካንድ ፡ አገር ፡ ወዳንዱ ፡ አገር ፡ የሚሰድድ ፡
ሌባን ፡ የሚዋሰው ፡ የለም ፡ ንብረትና ፡ ቤት ፡
የሌለው ፡ በመሸበት ፡ የሚያድር ፡ ሰውንም ፡
እንደዚሁ ፡ የሚዋሰው ፡ የለም ።

ምዕራፍ ፡ ፴፯ ።

፩ ወዳጅ ፡ ያበጀ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ወዳጅ ፡ አበጀሁ ፡
ይላል ፡ ነገር ፡ ግን ፡ በከንቱ ፡ ለስም ፡ ወዳጅ ፡
የሚሆን ፡ ሰው ፡ አለ ።
፪ በልቡናው ፡ ግን ፡ እስከሚሞትበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡
ኀዘን ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፡ ጠላትን ፡ የሚሆን ፡
ወዳጅም ፡ አለ ።
፫ ወይ ፡ መጥላት ፡ ሆይ ፡ ከወዴት ፡ ተገኘሽ ፡ በገሩ ፡
ሁሉ ፡ ኃጢአትን ፡ መላሽ ።
፬ በተድላ ፡ በደስታህ ፡ ጊዜ ፡ የሚቀርብህ ፡ ወዳጅ ፡
አለ ፡ ብትቸገር ፡ ግን ፡ እሱ ፡ ጠላት ፡ ይሆንሃል ።
፭ በበሽታህ ፡ ጊዜ ፡ ስለ ፡ ሆዱ ፡ የሚያዝንልህ ፡
ወዳጅ ፡ አለ ፡ የወነጀለህ ፡ ሰው ፡ ቢኖር ፡ ግን ፡
ይጠላህ ፡ ዘንድ ፡ እሱ ፡ ይቀድማል ።
፮ በተዘጋጀህ ፡ ጊዜ ፡ ወዳጅህን ፡ አትርሳ ፡ ገንዘ
ብም ፡ ብታገኝ ፡ አትተወው ።
፯ መክር ፡ ሁሉ ፡ ምክርን ፡ ይመክራል ፡ ነገር ፡ ግን ፡
ራሱን ፡ ይጠቅም ፡ ዘንድ ፡ የሚመክር ፡ ሰው ፡
አለ ።
፰ ከሚመክርህ ፡ ሰው ፡ ልቡናህን ፡ ጠብቅ ፡ ስለ ፡
ራሱ ፡ ይመክርሃልና ፡ በሚወድህ ፡ ገንዘብ ፡ አስ
ቀድመህ ፡ ግዳጁን ፡ እወቅበት ።
፱ በን ፡ ነገር ፡ አደረግህ ፡ ይልሃል ፡ ገንዘብህን ፡
የሚያጠፋብህን ፡ ነገር ፡ ያመጣብሃል ፡ በተቸገ
ርህም ፡ ጊዜ ፡ አይቶ ፡ ይስቅብሃል ።
፲ ከሚጠባበቅህ ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ አትማክር ፡ ከሚ
መራመርህም ፡ ሰው ፡ ነገርህን ፡ ሠውር ።
፲፩ በምታስቀናት ፡ ገንዘብ ፡ ከሴት ፡ ጋራ ፡ አትናገር ፡
የሰልፍን ፡ ነገር ፡ ከፈሪ ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ አትማ
ክር ፡ የትርፍን ፡ ነገር ፡ ከቅርብ ፡ ነጋዴ ፡ ጋራ ፡
አትማክር ፡ የንግድንም ፡ ነገር ፡ ከሩቅ ፡ ነጋዴ ፡
ጋራ ፡ አትማክር ። የምጽዋትንም ፡ ነገር ፡ ከን
ፉግ ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ አትማክር ። የሃይማኖትህ
ንም ፡ ነገር ፡ ዋጋ ፡ ለማስቀረት ፡ ከመናፍቅ ፡ ጋራ ፡
አትማክር ፡ የሥራንም ፡ ነገር ፡ ከሰነፍ ፡ ሰው ፡
ጋራ ፡ አትማክር ፡ ጨክኖ ፡ የመሥራትንም ፡
ነገር ፡ ከምንደኛ ፡ ጋራ ፡ አትማክር ። የጥበብ
ንም ፡ ነገር ፡ ከማያውቅ ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ አትማክር ፡
ቤተ ፡ ሰብህን ፡ ግዛ ፡ አበዝነህም ፡ አታኑረው ፡
ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ከዚህም ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ የምትማ
ከረው ፡ ነገር ፡ አይኑር ።
ሃይማኖት ፡ እንዳለው ፡ ከምታውቀው ፡ እግዚ ፲፪
አብሔርንም ፡ ከሚፈራ ፡ ልቡናውም ፡ እንደ ፡
ልብህ ፡ ከሆነ ፡ ከውነተኛ ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ ምክ
ርህን ፡ ተናገር ፡ ብታዝንም ፡ አዘንህን ፡ ከሚያ
ዝን ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ ተናገር ።
ከፍጹማን ፡ ሕዋሳት ፡ ይልቅ ፡ የሰው ፡ ልቡናው ፡ ፲፫
የምታገኘውን ፡ ነገር ።
የምታሳስበው ፡ ስለሆነ ፡ እሷ ፡ ከሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ፲፬
የታመነች ፡ ወዳጅህ ፡ ናትና ፡ ከሷ ፡ ጋራ ፡ የልቡ
ናህን ፡ ምክር ፡ አጽና ።
በውነትና ፡ በሚገባ ፡ ሥራህን ፡ ያቀናት ፡ ዘንድ ፡ ፲፭
ከዚህ ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
ለምን ።
የሥራው ፡ ሁሉና ፡ የነገረ ፡ ግዳጅ ፡ መጀመሪያ ፡ ፲፮
ምክር ፡ ነው ።
ለኀዘንም ፡ ቢሆን ፡ ለደስታም ፡ ቢሆን ፡ ለሞ ፲፯
ትም ፡ ቢሆን ፡ ለሕይወትም ፡ ቢሆን ።
የሰው ፡ ልቡናው ፡ አራቱን ፡ ማዕዘን ፡ ይመለከ ፲፰
ታል ፡ እነዚህንም ፡ ሁሉ ፡ አንደበት ፡ ያመጣቸ
ዋል ።
ሁሉን ፡ የሚማር ፡ ብዙ ፡ ምሥጢርም ፡ የሚያ ፲፱
ውቅ ፡ ሰው ፡ አለ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ሰውነቱን ፡ መጥ
ቀም ፡ አይችልም ።
በነገር ፡ እየተራቀቀ ፡ ራሱን ፡ የሚያስጠላ ፡ ፳
ሰው ፡ አለ ፡ እግዚአብሔር ፡ የዕንቍን ፡ መው
ደድ ፡ አይሰጠውምና ፡ ከጥበቡም ፡ ሁሉ ፡ ወጥ
ቷልና ።
እንደዚህ ፡ ያለውን ፡ ሰው ፡ ጥቅሙ ፡ ሁሉ ፡ ያል ፳፩
ፈዋል ።
ለሰውነቱ ፡ የሚራቀቅ ፡ በቃሉም ፡ የዋህ ፡ የሚ ፳፪
ሆን ፡ ሰው ፡ አለ ።
አዋቂ ፡ ሰው ፡ ወገኖቹን ፡ ይመክራቸዋል ፡ ለዘ ፳፫
መዶቹም ፡ ጥበብን ፡ ያስተምራቸዋል ።
ብልህ ፡ ሰው ፡ ከእግዚአብሔር ፡ በረከት ፡ ይጠ ፳፬
ግባል ፡ ያዩትም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ያደንቁታል ።
የእስራኤል ፡ ዘመናቸው ፡ በቍጥር ፡ ነው ፡ የእስ ፳፭
ራኤል ፡ ዘመናቸው ፡ ግን ፡ የማይቈጠር ፡ ነው ።
ወገኖቹን ፡ የሚያስተምር ፡ ሰው ፡ ዋጋውን ፡ ይቀ ፳፮
በላል ፡ ስሙም ፡ ለዘላለም ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ።
ልጄ ፡ በሕይወት ፡ ሳለህ ፡ ሰውነትህን ፡ ፍተናት ፡ ፳፯
የሚጐዳትን ፡ እወቅ ፡ ሁሉ ፡ የሚገባት ፡ አይደ
ለምና ፡ ሁሉም ፡
ለሰውነት ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኛት ፡ አይደለ ፳፰
ምና ፡ የወደደችውን ፡ ሁሉ ፡ አትስጣት ።

፳፱ ለመብል ፡ ሁሉ ፡ አትስስት ፡ ላየኸውም ፡ እህል ፡ ሁሉ ፡ አትሳሳ ።
፴ ብዙ ፡ መብላት ፡ ደዌ ፡ ይሆናልና ፡ ስስትም ፡ ጓታን ፡ ያበዛዋልና ፡ አትሳሳ ።
፴፩ ስስት ፡ የገደላቸው ፡ ሰዎች ፡ ብዙ ፡ ናቸው ፡ መጥኖ ፡ የሚበላ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ሰውነቱ ፡ ጤና ፡ ነው ።

ምዕራፍ ፡ ፴፰ ።

፩ እሱን ፡ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ መረጠው ፡ ጌትነቱ ፡ እንደ ፡ እጁ ፡ ሥራ ፡ ነውና ፡ ባለመድኃኒትን ፡ አክብረው ።
፪ ሕይወት ፡ ከእግዚአብሔር ፡ የሚገኝ ፡ ሲሆን ፡ ድርጎውን ፡ ከንጉሥ ፡ ይቀበላል ።
፫ ባለመድኃኒትን ፡ በጥበቡ ፡ ያከብሩታል ፡ በመኳንንትም ፡ ዘንድ ፡ ይመሰገናል ።
፬ እግዚአብሔር ፡ መድኃኒትን ፡ ከምድር ፡ ፈጥሯልና ፡ አዋቂ ፡ ሰው ፡ ባለመድኃኒትን ፡ አይንቀውም ።
፭ ታምራቱን ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ፡ ውሃ ፡ በእንጨት ፡ የጣፈጠ ፡ አይደለምን ።
፮ በታምራቱ ፡ ይከብሩ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሰዎች ፡ ጥበብን ፡ ሰጣቸው ።
፯ በመድኃኒቱ ፡ ያድናቸዋል ፡ በሽታቸውንም ፡ ያርቅላቸዋል ።
፰ በሚያድኑ ፡ ገንዘብ ፡ ከነሳቸው ፡ መድኃኒት ፡ ያደርጋሉ ፡ እሱም ፡ ለሀገር ፡ ፍቅርን ፡ ያመጣል ።
፱ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለምን ፡ እንጂ ፡ ልጄ ፡ በሽታህን ፡ ቸል ፡ አትበል ፡ እሱ ፡ ከደዌህ ፡ ይፈውስሃል ።
፲ ኀጢአትን ፡ ተዋት ፡ እደ ፡ ልቡናህን ፡ አቅና ፡ ልቡናህንም ፡ ከኀጢአት ፡ ሁሉ ፡ አንፃ ።
፲፩ መባዕህን ፡ አግባ ፡ አስበህ ፡ ስንዴህን ፡ አግባ ፡ የተቻለህን ፡ ያህል ፡ መሥዋዕትህን ፡ አብዝተህ ፡ አቅርብ ።
፲፪ እግዚአብሔር ፡ እሱን ፡ መርጦታልና ፡ ለባለ መድኃኒት ፡ ሥራውን ፡ ሥራለት ፡ እሱን ፡ ትሻዋለህና ፡ ካንተ ፡ አታርቀው ።
፲፫ በጃቸው ፡ ድኅነት ፡ የሚደረግበት ፡ ጊዜ ፡ አለና ።
፲፬ ይረዳቸው ፡ ዘንድ ፡ ዕረፍትንም ፡ ይሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ እነሳቸው ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ይለምናሉና ፡ አንተ ፡ አታርቀው ።
፲፭ እግዚአብሔርን ፡ የበደለ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ባለመድኃኒትን ፡ አግመኝ ፡ ተኵሰኝ ፡ ብሎ ፡ በባለመድኃኒት ፡ እጅ ፡ ይወድቃል ።
፲፮ ልጄ ፡ ለሞተ ፡ ሰው ፡ አልቅስለት ፡ እዘንለት ፡ ራስህንም ፡ አሳዝን ፡ እንደ ፡ አገሩም ፡ ግዕዝ ፡ ተዝካር ፡ አውጣለት ። ያገለገለህን ፡ ሰው ፡ ሞት ፡ ቸል ፡ አትበል ።
፲፯ ምር ፡ ብለህ ፡ አልቅስለት ፡ እጽንተህም ፡ እዘንለት ፡ እንደ ፡ አገሩም ፡ ግዕዝ ፡ አልቅስለት ፡ ስለ ፡ አገሩም ፡ ግዕዝ ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ሁለት ፡ ቀን ፡ አልቅስለት ።
፲፰ የብስጭት ፡ ኀዘን ፡ ኃይል ፡ የሚያደክም ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ስለ ፡ ብስጭት ፡ ኀዘን ፡ እንዳይገባህ ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ልቅሶህን ፡ ተው ።
የብስጭት ፡ ኀዘን ፡ ትካዝ ፡ ለሞት ፡ ያደርሳል ፡ የድሀ ፡ ዘመኑ ፡ ሁሉ ፡ በብስጭት ፡ ኀዘን ፡ ያልቃል ። ፲፱
የብስጭት ፡ ኀዘን ፡ ወደ ፡ ልቡናህ ፡ አታግባ ፡ የብስጭት ፡ ኀዘንን ፡ ካንተ ፡ አርቃት ። ፳
ድኅነት ፡ እንደሌለበት ፡ እወቅ ፡ ራስህን ፡ ታሳዝናለህ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ የምትጠቀመው ፡ ነገር ፡ የለም ። ፳፩
እኔ ፡ የተቀበልሁትን ፡ ዋጋ ፡ አስተውል ፡ አንተም ፡ እንደዚሁ ፡ ዋጋ ፡ እንድትቀበል ፡ እወቅ ። እኔ ፡ ዛሬ ፡ ብቀበል ፡ አንተም ፡ ነገ ፡ እንድትቀበል ፡ እወቅ ። ፳፪
የሞተ ፡ ሰውስ ፡ ዐረፈ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ነፍሱ ፡ ታርፍ ፡ ዘንድ ፡ ተዝካር ፡ አውጣለት ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ልቅሶህን ፡ ተው ። ፳፫
የጸሐፊ ፡ ጥበቡ ፡ በተሾመበት ፡ ወራት ፡ ይታወቃል ፡ ሥራውን ፡ የሚያበዛ ፡ ሰው ፡ አይራቀቅም ። ፳፬
ዕርፉን ፡ የሚያጸና ፡ ሰው ፡ በምንም ፡ በምን ፡ አይራቀቅም ፡ በርሻው ፡ ይታበያል ፡ በሬውን ፡ ይገርፋል ፡ በሥራውም ፡ ይመላለሳል ፡ ነገሩ ፡ ሁሉ ፡ አበት ፡ በሬና ፡ ወይፈን ፡ መግረፍ ፡ ነው ። ፳፭
ሐሳቡ ፡ እርሻውን ፡ እንዲያርስ ፡ ነው ፡ ትጋቱም ፡ በሬውን ፡ ገለባ ፡ ያበላ ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡ ወይፈኑንም ፡ እስኪያቀና ፡ ድረስ ፡ ይደክማል ። ፳፮
ሌሊቱ ፡ ቀን ፡ የሚሆንባቸው ፡ የጠራቢዎች ፡ አለቃና ፡ እንጨት ፡ ጠራቢም ፡ እንደሱ ፡ ናቸው ፡ የማኅተም ፡ ቅርጽ ፡ የሚቀርጹ ፡ የሚያለዝቡም ፡ ሰዎች ፡ እንደሱ ፡ ናቸው ፡ አሳቡም ፡ ሁሉ ፡ በየመልኩ ፡ መስሎ ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡ ምክሩ ፡ ሁሉ ፡ ማኅተሙን ፡ ማለዘብ ፡ ይጠነቀቅ ፡ ዘንድ ፡ ነው ። ፳፯
በወናፍ ፡ አጠገብ ፡ የሚቀመጥ ፡ የብረትም ፡ ሥራ ፡ የሚማር ፡ አንጥረኛ ፡ እንደሱ ፡ ነው ። የወናፉም ፡ ጢስ ፡ ሰውነቱን ፡ ያሸክረዋል ። እሳቱም ፡ ሰውነቱን ፡ እንደ ፡ ሰም ፡ ያቀልጣታል ፡ የመዶሻውም ፡ ድምጥ ፡ ጆሮውን ፡ ያደነቍረዋል ። ዓይኖቹም ፡ ባለጸጋ ፡ የሚሆንበትን ፡ ሥራ ፡ ይመለከታሉ ፡ በልቡም ፡ ሥራውን ፡ ይጨርስ ፡ ዘንድ ፡ ያስባል ፡ ትጋቱም ፡ ባለጸጋ ፡ የሚሆንበትን ፡ ሥራና ፡ ወናፉን ፡ ያሳምር ፡ ዘንድ ፡ ነው ። ፳፰
በሥራው ፡ የሚቀመጥ ፡ ሸክላ ፡ ሠሪም ፡ እንደሱ ፡ ነው ፡ በእግሩም ፡ መንኰራኵሩን ፡ ያዞራል ፡ ሥራውንም ፡ ይጨርስ ፡ ዘንድ ፡ ሁልጊዜ ፡ ያስባል ። የሠራውንም ፡ ሁሉ ፡ ይቈጥራል ። ፳፱
በእጁም ፡ ጭቃውን ፡ መስሎ ፡ ይሠራል ፡ በእግሩ ፡ ጭቃውን ፡ ሲረግጥ ፡ ኃይሉን ፡ ያደክማል ፡ የልቡናውም ፡ አሳብ ፡ ሥራውን ፡ ይጨርስ ፡ ዘንድ ፡ ነው ። ትጋቱም ፡ መወልወያውን ፡ ያዞር ፡ ዘንድ ፡ ነው ። ፴
እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ የጃቸውን ፡ ሥራ ፡ ተስፋ ፡ ያደርጋሉ ፡ ሁሉ ፡ በሥራቸው ፡ ይራቀቃሉ ። ፴፩

፴፪፤ ያለነሱቸውም ፡ ባገር ፡ መኖር ፡ አይቻልም ።
፴፫፤ ነገር ፡ ግን ፡ በሸንጎ ፡ ምክርን ፡ አያስመክሯ
ቸውም ፡ በደብባይም ፡ ከመኳንንት ፡ ጋራ ፡ አያ
ስቀምጧቸውም ፡ የቅጣት ፡ ፍርድንም ፡ አያስ
ፈርዷቸውም ፡ አያስገዟቸውም ፡ አያሠለጥኗ
ቸውም ።
፴፬፤ ያገርን ፡ ፈቃድ ፡ ያጸናሉ ፡ እንጂ ፡ ነገርን ፡
መስለው ፡ በመናገር ፡ አይኖሩም ፡ ጸሎታቸውም ፡
በሥራቸውም ፡ ይራቀቃ ፡ ዘንድ ፡ ነው ።
፴፭፤ ዕውቀት ፡ ግን ፡ በልቡ ፡ ለሚተጋ ፡ ሰው ፡ ነው ።
የእግዚአብሔርንም ፡ ሕግ ፡ ለሚያስብ ፡ ሰው ፡
ነው ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፱ ።

፩፤ ጥበብስ ፡ በቀደሙ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ዘንድ ፡
ተመረመረች ።
፪፤ በሃይማኖት ፡ ስማቸውን ፡ ላስጠሩም ፡ ሰዎች ፡
ትንቢትን ፡ ታስተምራለች ፡ ወደ ፡ ነቢያትም ፡
ምሳሌ ፡ ታገባለች ።
፫፤ የተሠወረውንም ፡ ምሳሌ ፡ ትመረምራለች ፡ ንብ
ቡንም ፡ ወደ ፡ ትርጓሜ ፡ ትመልሳለች ።
፬፤ በመኳንንትም ፡ መካከል ፡ ሰውን ፡ ትጠቅማ
ለች ፡ ባለቆችም ፡ መካከል ፡ እንዲታዩ ፡ ታደር
ጋለች ፡ ልዩ ፡ ወደ ፡ ሆኑ ፡ ወደ ፡ አሕዛብም ፡
አገር ፡ ታገባለች ።
፭፤ የሰዎች ፡ መፈጠር ፡ በበጎም ፡ በክፉም ፡ ነውና ።
በንስሐ ፡ ወደ ፡ ፈጣሪው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
ፈጥኖ ፡ ይሄድ ፡ ዘንድ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
ይለምን ፡ ዘንድ ፡ ልቡናውንም ፡ ገልጦ ፡ ይለ
ምን ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ኃጢአቱም ፡ ይለማመጥ ፡
ዘንድ ፡ ልቡናውን ፡ በንስሐ ፡ ወደ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ መለሰ ።
፮፤ ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ከወደደው ፡ ጥበብ ፡
የሚገልጥ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስንም ፡ ካሳደረበት ፡
እሱ ፡ የጥበቡንም ፡ ነገር ፡ ከገለጸለት ፡ ያ ፡ ሰው ፡
ደግ ፡ ሰው ፡ ነው ፡ በጸሎቱም ፡ ለእግዚአብሔር ፡
ይገዛል ።
፯፤ እሱም ጥበብንና ፡ ምክር ፡ ይገልጥለታል ፡ የተ
ሠወረውንም ፡ ይገልጥ ፡ ዘንድ ፡ ያሳስበዋል ።
፰፤ እሱም ፡ የትምህርቱን ፡ ጥበብ ፡ ያሳያል ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ምሎ ፡ በሠራው ፡ ሕጉ ፡ ይመካል ።
፱፤ ስለ ፡ ጥበቡም ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ያመሰግኑታል ፡
ስም ፡ አጠራሩም ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ፈጽሞ ፡ አይ
ጠፋም ፡ ስሙም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖ
ራል ።
፲፤ አሕዛብም ፡ ጥበቡን ፡ ይናገራሉ ፡ በሸንጎም ፡
መካከል ፡ ያመሰግኑታል ።
፲፩፤ ከሽህ ፡ ልጅ ፡ ስምን ፡ ማስጠራት ፡ ይሻላል ፡
ከሞቱም ፡ በኋላ ፡ ሥራው ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ።
፲፪፤ ዳግመኛም ፡ አስቤ ፡ እናገራለሁ ።
፲፫፤ የደጋግ ፡ ሰዎች ፡ ልጆች ፡ ስሙኝ ፡ በረድኤት ፡
ታደሉ ፡ አበባ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ጠል ፡ እንዲያ
ብብ ፡ እንደሱ ፡ አብቡ ። (በረድኤት ፡ ታደሉ ፡)
፲፬፤ የሽቱ ፡ መዓዛ ፡ ደስ ፡ እንዲያሰኝ ፡ መዓዛ ፡ ትም
ህርታችሁ ፡ እንደዚያ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ይሁን ።
ረዳ ፡ የሚባል ፡ አበባም ፡ ደስ ፡ እንዲያሰኝ ፡
ምግባራችሁ ፡ ሃይማኖታችሁ ፡ እንደዚያ ፡ ደስ ፡
የሚያሰኝ ፡ ይሁን ፡ መዓዛ ፡ ትምህርታችሁ ፡
ያማረ ፡ የተወደደ ፡ ይሁን ፡ ምስጋናውን ፡ ተና
ገሩ ፡ እግዚአብሔርንም ፡ በሥራው ፡ ሁሉ ፡
አመስግኑት ።
ስሙን ፡ አግኑት ፡ በምግባር ፡ በሃይማኖት ፡ ጸን ፲፭፤
ታችሁ ፡ ለጌትነቱም ፡ ተገዙ ፡ በመስገናችሁ
ትም ፡ ጊዜ ፡ እንዲህ ፡ በሉ ።
የእግዚአብሔር ፡ ሥራው ፡ ገናና ፡ ነው ፡ በሉ ። ፲፮፤
ይልቁንም ፡ ያማረ ፡ ነው ፡ በሉ ፡ ሥራቱ ፡
ሁሉ ፡ በየጊዜው ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ።
ይህ ፡ ለምንድነው ፡ ያለ ፡ ለምንድነው ፡ ይሉ ፡ ፲፯፤
ዘንድ ፡ አይገባም ፡ ሁሉም ፡ በየጊዜው ፡ ይወደ
ዳል ፡ ውኃውን ፡ በቃሉ ፡ እንደ ፡ ግድግዳ ፡
አጸናው ።
ነጠላ ፡ ፍጥረት ፡ አድርጎ ፡ የፈጠረው ፡ የለም ። ፲፰፤
የሰው ፡ ሁሉ ፡ ሥራ ፡ በፊቱ ፡ ነው ፡ በፊቱም ፡ ፲፱፤
መሠወር ፡ የሚችል ፡ የለም ።
ዓለም ፡ ሳይፈጠር ፡ እስከ ፡ ዘለዓለም ፡ ድረስ ፡ ፳፤
ሁሉን ፡ አወቀ ፡ በፊቱ ፡ ምንም ፡ ልዩ ፡ ፍጥረት ፡
የለም ።
ሁሉ ፡ በሥላሴ ፡ ፈቃድ ፡ ተፈጥሯልና ፡ ይህ ፡ ፳፩፤
ለምንድነው ፡ ያለ ፡ ለምንድነው ፡ የሚል ፡ የለም ።
በረከቱም ፡ እንደፈሳሽ ፡ ውኃ ፡ መላች ፡ እንደ ፡ ፳፪፤
ጥፋት ፡ ውኃ ፡ ምድርንም ፡ ከፈተቻት ።
እንደዚሁ ፡ ፍርዱ ፡ አሕዛብን ፡ አጠፋቻቸው ። ፳፫፤
የውነተኛ ፡ ሰው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ የቀና ፡ ነው ፡ ፳፬፤
የኃጢአተኛ ፡ ሰው ፡ ሥራ ፡ ግን ፡ መሰናክል ፡
ነው ፡ ውኃውንም ፡ ለውጦ ፡ ያጸናው ፡ እሱ ፡
ነው ።
በጎ ፡ ነገር ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ ለበጎ ፡ ሰዎች ፡ ፳፭፤
ተፈጠረች ፡ እንደዚሁ ፡ ክፉ ፡ ነገርም ፡ ለኃጢ
አተኞች ፡ ተፈጠረች ።
የሰው ፡ የፈቃዱ ፡ መጀመሪያ ፡ ውኃ ፡ እሳት ፡ ፳፮፤
ብረት ፡ ጨው ፡ እህል ፡ ስንዴ ፡ ማር ፡ ወተት ፡
የወይን ፡ ዘለላ ፡ ደም ፡ ዘይት ፡ ልብስ ፡ ነው ።
ይህ ፡ ሁሉ ፡ ለደጋግ ፡ ሰዎች ፡ በረከታቸው ፡ ነው ፡ ፳፯፤
እንደዚሁም ፡ ሁሉ ፡ በኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡
በክፉ ፡ ይመለስባቸዋል ።
ሊበቀሉባት ፡ የተፈጠረች ፡ ፍጥረት ፡ አለች ፡ ፳፰፤
በኃጢአታቸው ፡ መቅሠፍታቸውን ፡ ያበዚ
ታል ፡ በዘመናቸው ፡ ኃይላቸው ፡ ይደክማል ፡
የፈጣሪያቸው ፡ መቅሠፍትም ፡ ለማጥፋት ፡
ይመጣባቸዋል ።
እሳት ፡ በረድ ፡ ረኃብ ፡ ቸነፈር ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ ፳፱፤
ሊበቀሉበት ፡ ተፈጠረ ።
የምድር ፡ አበቦች ፡ ጥርስ ፡ ጊንጥ ፡ እፉኝት ፡ ፴፤
ይህ ፡ ሁሉ ፡ ሊበቀሉበት ፡ ተፈጠረ ፡ ጦርም ፡
ኃጢአተኞችን ፡ ታጠፋቸው ፡ ዘንድ ፡ ተዘጋ
ጀች ።
እሱ ፡ ግን ፡ በይቅርታው ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ፡ የዓለ ፴፩፤
ምንም ፡ ፈቃድ ፡ ያዘጋጃል ። ሁሉም ፡ የሚጦ

ትበት ፡ ሰዓት ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ ከጊዜው ፡ አያ
ልፍም ።
፴፪ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ዓለም ፡ ከተፈጠረ ፡ ጀምሮ ፡
ሁሉም ፡ ተዘጋጀ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፍጥረት ፡
ሁሉ ፡ ያማረ ፡ ነውና ፡ ይኸንን ፡ አስቤ ፡ በመጽ
ሐፍ ፡ ጻፍሁት ።
፴፫ ለሰውም ፡ በየጊዜው ፡ ፈቃዱን ፡ ይሰጣል ።
፴፬ ሁሉን ፡ የሚሞትበት ፡ ቀን ፡ ይነዳዋልና ፡ ይህን ፡
መልክም ፡ አድርገህ ፡ ያንን ፡ ክፉ ፡ አድርገህ ፡
ፈጠርህ ፡ የሚለው ፡ የለም ።
፴፭ አሁንም ፡ በፍጹም ፡ ልቡናችሁ ፡ በፍጹም ፡ አን
ደበታችሁ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑት ፡
ስሙንም ፡ ሁለጊዜ ፡ አመስግኑት ።

## ምዕራፍ ፡ ፵ ።

፩ በሰው ፡ ተፈጥሮ ፡ ያለ ፡ ሞትን ፡ መጠራጠር ፡
ጽኑ ፡ ነው ፡ ከናታቸው ፡ ሆድ ፡ ከተወለዱ ፡ ጀምሮ ፡
በሁሉ ፡ እናት ፡ በመቃብር ፡ ሆድ ፡ እስኪቀበሩ ፡
ድረስ ፡ በአዳም ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ የከበደ ፡ ሸክም ፡
ሞት ፡ አለ ።
፪ የምታስደነግጥ ፡ ናት ፡ ልብንም ፡ የምታስፈራ ፡
ናት ፡ በመንግሥት ፡ ዙፋን ፡ካለ ፡ ንጉሥ ፡ ጀምሮ ፡
በመድና ፡ በትቢያ ፡ ላይ ።
፫ እስከሚተኛ ፡ ድሀ ፡ ድረስ ፡ ዕለተ ፡ ሞትን ፡
መጠራጠር ፡ በአዳም ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ ሁሉ ፡
አለ ።
፬ ቍጣ ፡ ቅናት ፡ ንዝንዝ ፡ ሰውን ፡ ማወክ ፡ ሞትን ፡
መፍራት ።
፭ ክርክር ፡ ሰውን ፡ ማማት ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ በሰው ፡
ልቡና ፡ አለ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ በመኝታው ፡ በተኛ ፡
ጊዜ ፡ የሌሊት ፡ እንቅልፍ ፡ አሳቡን ፡ ይለውጠ
ዋል ።
፮ ዕረፍቱም ፡ እንደ ፡ ኢምንት ፡ ጥቂት ፡ ነው ፡
ይህ ፡ ሁሉ ፡ በመኝታው ፡ ይታወቃል ፡ አንድ ፡
ጊዜ ፡ እንደ ፡ ሽንኅ ፡ ተከማችቶ ፡ ያገኘዋል ፡
የልቡናውን ፡ ምክር ፡ የሚያወላውላት ፡ ሰው ፡
በሰልፍ ፡ እንድሚሸሽ ፡ ሰው ፡ ነው ።
፯ የሸሸ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ዕለቱን ፡ ከሞት ፡ ያመል
ጣል ፡ ፍርሃቱንም ፡ እሱ ፡ ይናገራታል ።
፰ ይህ ፡ ሁሉ ፡ እስከ ፡ ከብት ፡ ድረስ ፡ በሰው ፡
ላይ ፡ አለ ፡ ይህም ፡ በኃጢአኞች ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡
ሰባት ፡ እጥፍ ፡ ይብሳል ።
፱ ሰልፍ ፡ መታበይ ፡ ቸነፈር ፡ ጦር ፡ ቀጠና ፡
የልብ ፡ ቍስል ፡ መቅሠፍት ።
፲ ይህ ፡ ሁሉ ፡ በኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ ተፈ
ጠረ ፡ ስለነሳቸውም ፡ ኃጢአት ፡ የጥፋት ፡ ውኃ ፡
መጣ ።
፲፩ ሁሉ ፡ ከምድር ፡ ተፈጠረ ፡ ሁሉም ፡ ወደ ፡ ምድር ፡
ይመለሳል ፡ የወንዙ ፡ ውኃ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ውቅ
ያኖስ ፡ ይመለሳል ።
፲፪ ሰዎችም ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ይመለሳሉ ፡
ክሕደት ፡ ትጠፋለች ፡ ሃይማኖት ፡ ግን ፡ ለዘለዓ
ለሙ ፡ ትጸናለች ።
፲፫ ሥርቆ ፡ ቀምቶ ፡ ያጠራቀሙት ፡ ገንዘብ ፡ እንደ ፡
ፈሳሽ ፡ ውኃ ፡ ፈጥኖ ፡ ይጠፋል ፡ ዝናም ፡ በዘ
ነመ ፡ ጊዜ ፡ መብረቅ ፡ ተሰምቶ ፡ እንዲጠፋ ፡
እንደዚያ ፡ ፈጥኖ ፡ ይጠፋል ።
እግዚአብሔር ፡ ሥልጣኑን ፡ በገለጠ ፡ ጊዜ ፡ ፲፬
ደስ ፡ ያሰኛል ፡ የሚክዱት ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ፈጽ
መው ፡ ይጠፋሉ ።
የኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ ልጆች ፡ ልጆቻቸው ፡ ፲፭
አይበዙም ፡ የኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ አበትነታ
ቸው ፡ በሚያድጥ ፡ አለት ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ወደቀ ፡
ዘር ፡ ነው ።
ዝናም ፡ በሁሉ ፡ ላይ ፡ ይዘንማል ፡ በወንዝ ፡ዳር ፡ ፲፮
ያለ ፡ አኽያ ፡ ከሬላ ፡ ከቀጤማ ፡ ተለይቶ ፡ ተነቃ
ቅሎ ፡ እንዲወድቅ ፡ አበትነታቸው ፡ እንደዚያ ፡
ይጠፋል ።
የእግዚአብሔር ፡ ስጦታ ፡ ግን ፡ በበረከት ፡ ጊዜ ፡ ፲፯
እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ፈጠራት ፡ እንደ ፡ ገነት ፡
ነው ፡ ምጽዋትም ፡ ለዘላለሙ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ።
በገንዘብ ፡ የተዘጋጀ ፡ ሰው ፡ ሕይወቱ ፡ የበላው ፡ ፲፰
የጠጣው ፡ ቢስማማው ፡ ነው ፡ ከነዚህም ፡ ከሁ
ለቱ ፡ ይልቅ ፡ የተቀበረ ፡ ወርቅ ፡ ማግኘት ፡ ደስ ፡
ያሰኛል ።
ያገር ፡ ሕንፃና ፡ ልጆችም ፡ ስምን ፡ ያስጠራሉ ፡ ፲፱
ከነዚህም ፡ ከሁለቱ ፡ ይልቅ ፡ ልቡናዋ ፡ ያማረ ፡
ሴት ፡ ደስ ፡ ታሰኛለች ።
ዘፈንና ፡ ወይን ፡ ልቡናን ፡ ደስ ፡ ያሰኛሉ ፡ ከነ ፳
ዚህም ፡ ከሁለቱ ፡ ይልቅ ፡ ጥበብን ፡ መውደድ ፡
ደስ ፡ ያሰኛል ።
በገናና ፡ መሰንቆ ፡ ሰውነትን ፡ ደስ ፡ ያሰኛታል ፡ ፳፩
ከሁለቱም ፡ ይልቅ ፡ ልዝብ ፡ አንደበት ፡ ደስ ፡
ያሰኛል ።
ደም ፡ ግባት ፡ ከመልክ ፡ ጋራ ፡ ዓይንን ፡ ደስ ፡ ፳፪
ያሰኛታል ። ከሁለቱም ፡ ይልቅ ፡ ቡቃያ ፡ ደስ ፡
ያሰኛል ።
አማችና ፡ ወዳጅ ፡ በዘመናቸው ፡ ይጠቅማሉ ፡ ፳፫
ከሁለቱ ፡ ይልቅ ፡ ደግ ፡ ሴት ፡ ባሏን ፡ ደስ ፡ ታሰ
ኛዋለች ።
ረዳትና ፡ ወንድሞችም ፡ በመከራ ፡ ቀን ፡ ይጠ ፳፬
ቅማሉ ፡ ከሁለቱም ፡ ይልቅ ፡ ለማዳን ፡ ምጽዋት ፡
ትሻላለች ።
ብርና ፡ ወርቅ ፡ አገር ፡ ያጸናሉ ፡ ከሁለቱ ፡ ይልቅ ፡ ፳፭
በጎ ፡ ምክር ፡ ደስ ፡ ታሰኛለች ።
ገንዘብና ፡ ባለጸግነት ፡ ልቡናን ፡ ደስ ፡ ያሰኛሉ ፡ ፳፮
ከሁለቱ ፡ ይልቅ ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡
ይበልጣል ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ የም
ታሳጣው ፡ የለም ፡ አጋዥም ፡ አትሻ ።
እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ በረከቷ ፡ እግዚአ ፳፯
ብሔር ፡ እንደ ፡ ፈጠራት ፡ እንደ ፡ ገነት ፡ ናት ፡
ተድላ ፡ ደስታና ፡ ክብርም ፡ በሷ ፡ አለ ።
ልጄ ፡ በጉልበት ፡ ሳለህ ፡ ልመናን ፡ አትውደ ፳፰
ዳት ፡ ከመለመን ፡ ሞት ፡ ይሻላል ።
የሌላ ፡ ማዕድ ፡ ደጅ ፡ የሚጠና ፡ ተስፋ ፡ የሚያ ፳፱
ደርግ ፡ ሰው ፡ አነዋወሩ ፡ እንደ ፡ ሞት ፡ ሰው ፡
ነው ፡ እንጂ ፡ እንደ ፡ ደኅነኛ ፡ አይደለም ፡ የሰው ፡
እህል ፡ የሚወድ ፡ ሰው ፡ ከሐሜት ፡ አይድንም ፡

የተመከረ ፡ አዋቂ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ከሁሉ ፡ ይጠበ
ቃል ።
፴፤ ለማያፍር ፡ ሰው ፡ አፍ ፡ ልመና ፡ ያማረ ፡ ነው ፡
በሆዱ ፡ ግን ፡ እሳት ፡ ትነዳለች ።

ምዕራፍ ፡ ፵፩ ።

፩፤ በሕይወት ፡ ሳለ ፡ በሁሉ ፡ ተዘጋጅቶ ፡ ሳለ ፡
ኃይልም ፡ ሳለው ፡ ለመብላት ፡ ሆዱም ፡ ተከ
ፍቶ ፡ ሳለ ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ በመጣህ ፡ ጊዜ ፡ ሞት ፡
ስም ፡ አጠራርህ ፡ ምን ፡ ይከፋ ።
፪፤ ገንዘብ ፡ ሳይኖረው ፡ ፈጽሞም ፡ በረጅ ፡ የሚያ
ደርገውም ፡ ምንም ፡ ምን ፡ ሳይኖር ፡ የሚያው
ቀውም ፡ ሳይኖር ፡ በድሀ ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ በመጣህ ፡
ጊዜ ፡ ሞት ፡ ስም ፡ አጠራርህ ፡ ምን ፡ ያምር ።
፫፤ የሞትን ፡ ፍርድ ፡ አትፍራ ፡ የእግዚአብሔር ፡
ፍርድ ፡ ሞት ፡ በሰው ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ አለና ፡ ከንተ ፡
አስቀድሞ ፡ የነበሩትን ፡
፬፤ ከንተም ፡ በኋላ ፡ የሚነሡትን ፡ አስበቸው ። የእ
ግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ ሞትን ፡ ለምን ፡ ትነቅፋ
ለህ ፡ ሺህ ፡ ዘመንም ፡ ብትኖር ፡ ሕይወት ፡ የበ
ሕሪየ ፡ ነው ፡ ብለህ ፡ ከሞት ፡ ጋራ ፡ ክርክር ፡
የለህም ።
፭፤ የኃጢአተኞች ፡ ሰዎች ፡ ልጆች ፡ ጐስቋሎች ፡
ልጆችን ፡ ይሆናሉ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡
የዘነጉ ፡ ሰዎችም ፡ ቤታቸው ፡ ይፈርሳል ።
፮፤ የኃጢአተኞች ፡ ልጆች ፡ ራሳቸውን ፡ ያጣሉ ፡
ኃጢአታቸውም ፡ ከልጅቻቸው ፡ ጋራ ፡ አደገ ።
፯፤ ስለሱ ፡ ይዋረዳሉና ፡ የኃጢአተኛ ፡ አባት ፡
ልጆች ፡ ይጐሰቍላሉ ።
፰፤ የእግዚአብሔርን ፡ ሕግ ፡ ላፈረሳችሁ ፡ ኃጢአ
ተኞች ፡ ሰዎች ፡ ወዮላችሁ ።
፱፤ ብትወልዱም ፡ ለርግማን ፡ ትወልዳላችሁ ።
፲፤ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ከምድር ፡ ተፈጠረ ፡ ዳግመኛም ፡
በሞት ፡ መመለሳቸው ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ ነው ፡
ኃጢአተኞችም ፡ ሰዎች ፡ ከርግማን ፡ ወደ ፡
ሞት ፡ ይሄዳሉ ።
፲፩፤ የሰው ፡ ልቡናው ፡ በግዘፉ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፡
የኃጢአተኞች ፡ ሰዎችም ፡ ስማቸው ፡ ይጠፋል ።
፲፪፤ ስምህን ፡ ታስጠራ ፡ ዘንድ ፡ በጎ ፡ ስምን ፡ አስብ ፡
ከብዙ ፡ ወርቅ ፡ ድልብ ፡ እሱ ፡ ብቻ ፡ ይቀርሃል ።
፲፫፤ በዘመንህ ፡ ቍጥር ፡ በተድላ ፡ በደስታ ፡ መኖር ፡
ያማረ ፡ ነው ፡ እሱ ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖር
ልሃልና ፡ በጎ ፡ ስም ፡ ይሻላል ።
፲፬፤ ጥበብ ፡ ግን ፡ ልጆቼን ፡ በተድላ ፡ በደስታ ፡ ትጠ
ብቃቸዋለች ፡ የተሠወረ ፡ ጥበብ ፡ የማይታይ ፡
ድልብ ፡ የሁለቱ ፡ ጥቅማቸው ፡ ምንድነው ።
፲፭፤ ጥበቡን ፡ ከሚሠውር ፡ ሰው ፡ ስንፍናውን ፡ የሚ
ሸሽግ ፡ ሰው ፡ ይሻላል ።
፲፮፤ እንግዴህ ፡ ጥበቤንና ፡ ቃሌን ፡ እፈሩ ፡ በጎ ፡ ነገ
ርን ፡ የሚያፍር ፡ ሰው ፡ በበጎ ፡ ረድኤት ፡ ይጠ
በቃል ፡ በሁሉ ፡ ሊማከሩ ፡ ይገባል ፡ ነገር ፡ ግን ፡
ሁሉ ፡ የታመነ ፡ አይደለም ።
፲፯፤ ልጅ ፡ እንወልዳለን ፡ ብለው ፡ በገዘሙት ፡ መኖር ፡
ለናትና ፡ ላባቱ ፡ አፍረት ፡ ነው ፡ ለመኳንንትና ፡
ለአለቃም ፡ አሰት ፡ መፍረድ ፡ አይገባም ።
ለሹምና ፡ ለዳኛ ፡ ቃል ፡ መለወጥ ፡ አይገባም ፡ ፲፰፤
ለማኅበርና ፡ ለሕዝብም ፡ ከሕግ ፡ ወጥቶ ፡ መሳት ፡
አፍረት ፡ ነው ፡ ከሽሙርህና ፡ ከወዳጅህ ፡ ጋራ ፡
መከዳዳት ፡ አይገባም ።
ለእንግዳ ፡ ከደረበት ፡ ቦታ ፡ ሰርቆ ፡ መሄድ ፡ ፲፱፤
አፍረት ፡ ነው ፡ የሌላ ፡ ሰው ፡ እህል ፡ ለመብላት ፡
ጥቂት ፡ እህል ፡ ይዞ ፡ መቅረብ ፡ አይገባም ፡ ከበ
ልንጀራህ ፡ ገንዘብና ፡ ከደራ ፡ ገንዘብ ፡ መስረቅ ፡
አፍረት ፡ ነው ።
የሚጠራህን ፡ ሰው ፡ ቻል ፡ ማለት ፡ አይገባም ፡ ፳፤
የጐልማሳ ፡ ሚስትንም ፡ ማቃጠር ፡ አይገባም ።
በመከራው ፡ ጊዜ ፡ በልንጀራህን ፡ ቻል ፡ ማለት ፡ ፳፩፤
አፍረት ፡ ነው ፡ ለሌላ ፡ ገንዘብም ፡ መሳሳት ፡ አይ
ገባም ። የጐልማሳ ፡ ሚስት ፡ ማነጋገር ፡ አይገ
ባም ፡ እሰጥሻለሁ ፡ ብለህ ፡ አትከዳት ።
ልጅዋንም ፡ አታብብላት ፡ ወደ ፡ መኝታዋም ፡ ፳፪፤
አትቅረብ ፡ ከሰብኸው ፡ በኋላ ፡ በወዳጅህ ፡ መለ
ገድ ፡ አይገባም ፡ የወዳጅህን ፡ ምሥጢር ፡ ማው
ጣት ፡ አፍረት ፡ ነው ።
ይኸንን ፡ ከጠበቅህ ፡ በውነት ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፳፫፤
የሚያፍር ፡ ትሆናለህ ፡ በሰውም ፡ ሁሉ ፡ ዘንድ ፡
መወደድን ፡ ታገኛለህ ።

ምዕራፍ ፡ ፵፪ ።

ነገር ፡ ግን ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ አትፈር ፡ እግዚአ ፩፤
ብሔር ፡ በፍርድ ፡ አታድሉ ፡ ስላለ ፡ በደል ፡ እን
ዳይሆንብህ ፡ ለሰው ፡ ፊት ፡ አይተህ ፡ አታድላ ።
ይሙት ፡ በቃውን ፡ ይድን ፡ በቃ ፡ ብለህ ፡ እንዳ ፪፤
ትፈርድ ፡ ስለ ፡ ፍርድህና ፡ ስለ ፡ ሥራትህም ፡
አትፈር ።
ከሽሙርህ ፡ ጋራ ፡ ገንዘብህን ፡ በተቈጣጠርህ ፡ ፫፤
ጊዜ ፡ አትፈር ፡ ስለ ፡ ርስትህና ፡ ስለ ፡ ዋጋህም ፡
አትፈር ።
ስለ ፡ ላዳንና ፡ ስለሚዛንም ፡ ጥቂትም ፡ ብዙም ፡ ፬፤
ቢሆን ፡ ስለ ፡ ገንዘብህም ፡ አትፈር ።
ስለሚረባህ ፡ ስለሚጠቅምህም ፡ ሁሉ ፡ አትፈር ፡ ፭፤
ልጆችህንም ፡ ስለማስተማር ፡ አትፈር ፡ ክፉ ፡
ባሪያንም ፡ ጐን ፡ ጐኑን ፡ ግጠበው ።
ገንዘብ ፡ በምታበክን ፡ ሴት ፡ ቍልፍ ፡ መያዝ ፡ ፮፤
ያማረ ፡ ነው ፡ አገባቡም ፡ ብዙ ፡ ከሆነ ፡ ዘንድ ፡
በቍጥር ፡ አኑር ።
የምትሠራውን ፡ ሁሉ ፡ በቍጥር ፡ በሚዛንና ፡ በላ ፯፤
ዳን ፡ አድርግ ፡ ያወጣኸውና ፡ ያገባኸው ፡ ያነሣ
ኸው ፡ የሰጠኸው ፡ ሁሉ ፡ በደብዳቤ ፡ ይሁንህ ።
ሰነፍን ፡ ሰው ፡ አእምሮ ፡ የሌለውንም ፡ ሰው ፡ ፰፤
በረጅ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ገዘሙት ፡ የሚሄድ ፡ ሽማግሌ
ንም ፡ ስለመምከር ፡ አትፈር ፡ ይኸን ፡ ያደረግህ ፡
እንደሆነ ፡ በሰው ፡ ሁሉ ፡ ዘንድ ፡ በውነት ፡ ፈጽ
መህ ፡ አዋቂ ፡ ትሆናለህ ።
ሴት ፡ ልጅ ፡ ላባቷ ፡ የተሠወረ ፡ ቍርጥማት ፡ ፱፤
ናት ፡ እሷንም ፡ ማሰብ ፡ እንቅልፍ ፡ ያሳጣዋል ፡
በሕፃንነቷ ፡ ጀምረህ ፡ እስክታድግ ፡ ድረስ ፡
ጠብቃት ፡ ሳትባልቅም ፡ አጋባት ።

፲ ከገበችም ፡ በኋላ ፡ መክን ፡ እንዳትሆን ፡ ጸልይ
ላት ።
፲፩ የጠላትህ ፡ መዘባበቻ ፡ እንዳታደርግህ ፡ የማታ
ፍር ፡ ልጅን ፡ አጽንተህ ፡ ጠብቃት ፡ በብዙ ፡
ሰዎች ፡ መካከልም ፡ እንዳታሳፍርህ ፡ ለወገኖ
ችህ ፡ ወገን ፡ ለወዳጅህ ፡ ንገር ።
፲፪ ሰውን ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ መልኩ ፡ አታድላለት ፡ ወደ ፡
ሴቶችም ፡ መካከል ፡ አታግባው ።
፲፫ ከልብስ ፡ ብል ፡ ይገኛል ፡ ኃጢአትም ፡ ሁሉ ፡
ከሴቶች ፡ ይገኛል ።
፲፬ ከሴት ፡ ቸርነት ፡ የወንድ ፡ ንፍገት ፡ ይሻላል ፡
ውሽማዋንና ፡ በሷን ፡ የምታቃና ፡ ሴት ፡ አፍ
ረት ፡ ናት ።
፲፭ እንግዴህ ፡ ወዲህ ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔርን ፡
ሥራ ፡ አስባለሁ ፡ ያየሁትንም ፡ እናገራለሁ ፡
ፍጥረቱ ፡ ሁሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ተፈ
ጥሯልና ።
፲፮ ፀሐይ ፡ ያበራል ፡ ሁሉንም ፡ ያሳያል ፡ የእግዚአ
ብሔርም ፡ ብርሃኑ ፡ በሁሉ ፡ ምሉ ፡ ነው ።
፲፯ ተአምራቱን ፡ ሁሉ ፡ ይናገሩ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ለወዳጆቹ ፡ ፀሐይን ፡ አልፈጠረምን ፡
ይሉ ፡ ፍጥረቱን ፡ ያጸና ፡ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ነው ፡ ሁሉም ፡ በጌትነቱ ፡ ጸንቶ ፡
ይኖራል ።
፲፰ ልብንና ፡ ጥልቅንም ፡ መርምሮ ፡ ያውቃቸዋል ፡
ምክራቸውንም ፡ ሁሉ ፡ ያውቃል ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ የልቡና ፡ አሳብን ፡ ሁሉ ፡ ያውቃል ፡ የዓ
ለም ፡ ምልክት ፡ የሚሆን ፡ ጨረቃንም ፡ አይ ።
፲፱ ያለፈውንም ፡ የሚመጣውን ፡ እሱ ፡ ይናገራል ፡
የተሠወረውንም ፡ ምሥጢር ፡ ይገልጣል ።
፳ ከእግዚአብሔር ፡ ምክር ፡ ሁሉ ፡ የሚያመልጥ ፡
የለም ፡ ከነገሩ ፡ ሁሉ ፡ አንዲት ፡ ቃል ፡ ስንኳ ፡
የሚሠወረው ፡ የለም ።
፳፩ የመለኮቱ ፡ ክብር ፡ ለሥጋው ፡ ጌጥ ፡ አደረገ ፡
ይህቺም ፡ ቃል ፡ ዓለም ፡ ሳይፈጠር ፡ የነበረች ፡
ናት ፡ ለዘለዓለሙም ፡ ጸንታ ፡ ትኖራለች ፡ አትጨ
ምርም ፡ አትጐድልም ፡ አንድ ፡ መካርን ፡ ስንኳ ፡
አልፈለገም ።
፳፪ ፍጥረቱ ፡ ሁሉ ፡ ፈጽሞ ፡ ያማረ ፡ ነው ፡ ብርሃ
ንም ፡ እንደ ፡ መሆኑ ፡ ሊያዩት ፡ ያማረ ፡ ነው ።
፳፫ ይህ ፡ ሁሉ ፡ ለዘለዓለሙ ፡ በሕይወት ፡ ይኖራል ፡
የሚወዱትን ፡ ልመናቸውን ፡ ሁሉ ፡ ይሰማል ።
፳፬ አንዱም ፡ አንዱም ፡ ከንዱ ፡ ጋራ ፡ ሁለት ፡
ሁለት ፡ ሆኖ ፡ ተፈጠረ ፡ ምንም ፡ ምንም ፡ ነጠላ ፡
አድርጎ ፡ የፈጠረው ፡ የለም ።
፳፭ ለመብዛት ፡ አንዱን ፡ ከንዱ ፡ ጋራ ፡ አጸናው ፡
ፍጥረቱን ፡ ከማየት ፡ ማን ፡ ይጠግባል ።

ምዕራፍ ፡ ፵፫ ።

፩ ጠፈርን ፡ በህዋው ፡ ላይ ፡ አጸናት ፡ ሰማይ
ንም ፡ ማየት ፡ በፀሐይ ፡ ብርሃን ፡ ነው ።
፪ ብርሃኑን ፡ ያሳይ ፡ ዘንድ ፡ ፀሐይን ፡ ያወጣል ፡
የሰማይ ፡ ብርሃን ፡ ሥራትም ፡ ድንቅ ፡ ነው ።
፫ በዋዕዩም ፡ አገሩን ፡ ያቃጥላል ፡ ዋዕዩንስ ፡ ማን ፡
ይቋቋመዋል ።
ዋዕዩም ፡ እንደሚነድ ፡ እሳት ፡ ያቃጥላል ፡ የፀ ፬
ሐይ ፡ ሦስተኛ ፡ ብርሃኗ ፡ ተራሮችን ፡ ያቃጥላቸ
ዋል ። የእሳትም ፡ ዋዕይ ፡ ከሱ ፡ ይገኛል ፡ ብርሃ
ኑንም ፡ ማየት ፡ ዓይን ፡ ያጠምማል ።
የፈጠረው ፡ እግዚአብሔርም ፡ ደግ ፡ ነው ፡ በቃ ፭
ሉም ፡ ፈጥኖ ፡ ይሄዳል ።
ጨረቃም ፡ ለሰው ፡ ሁሉ ፡ ምልክት ፡ ነው ፡ ላገ ፮
ሩም ፡ ሁሉ ፡ ምልክት ፡ ነው ፡ በሷም ፡ ቀን ፡
ይለያል ።
በጨረቃም ፡ የበዓላቱ ፡ ምልክት ፡ ይታወቃል ፡ ፯
ሕፀፅ ፡ እያደረገ ፡ የሚያልቅ ፡ ብርሃን ፡ እሱ ፡
ነው ።
ጨረቃስ ፡ እንደ ፡ ስሟ ፡ ናት ፡ ከከዋክብትም ፡ ፰
እንድትበልጥ ፡ ድንቅ ፡ ነው ፡ በሰማይ ፡ ሠራ
ዊት ፡ በከዋክብት ፡ ሥራትም ፡ ሕፀፅንና ፡ ምላ
ትን ፡ እንድታፈራርቅ ፡ ድንቅ ፡ ነው ፡ በሰማይ ፡
ሠራዊት ፡ በከዋክብትም ፡ መካከል ፡ ሁና ፡ ታበ
ራለች ።
የሰማይ ፡ ጌጥ ፡ የከዋክብት ፡ ብርሃን ፡ ነው ። ፱
እግዚአብሔር ፡ በፈጠረው ፡ በጠፈር ፡ ሁነው ፡
ለዚህ ፡ ዓለም ፡ ያበራሉ ።
በጌትነቱም ፡ ቃል ፡ በየሥራቸውም ፡ ጸንተው ፡ ፲
ይኖራሉ ፡ ከሥራታቸውም ፡ ወጥተው ፡ አያል
ፉም ።
ብርሃኑ ፡ ፈጽሞ ፡ ያማረ ፡ ነውና ፡ ቀስተ ፡ ደመ ፲፩
ናውን ፡ አይተህ ፡ ፈጣሪውን ፡ አመስግነው ።
በሰማይ ፡ ይከፈላል ፡ ብርሃኑም ፡ ይከበዋል ፡ የእ ፲፪
ግዚአብሔርም ፡ ቃሉ ፡ ይከፍለዋል ።
በትእዛዙም ፡ በረድ ፡ ይዘንባል ፡ መብረቅም ፡ ፲፫
በፈቃዱ ፡ ፈጥኖ ፡ ይወርዳል ።
ስለዚህ ፡ ነገር ፡ እግዚአብሔር ፡ በቃውን ፡ ይገ ፲፬
ልጣል ፡ ደመናትም ፡ እንደ ፡ ወፎች ፡ ይበራሉ ።
በገናንነቱም ፡ ደመናትን ፡ ያጸናቸዋል ፡ የበረድ ፡ ፲፭
ድንጋይም ፡ ይከፈላል ።
በጉብኛቸውም ፡ ጊዜ ፡ ተራሮች ፡ ይነዋወጣሉ ፡ ፲፮
በፈቃዱም ፡ የምሥራቅ ፡ነፋስ ፡ ይነፍሳል ።
የመብረቁም ፡ ቃል ፡ ምድርን ፡ ያስፈራታል ፡ ፲፯
የምዕራብ ፡ ነፋስም ፡ ሰውነትን ፡ ያደርቃታል ፡
ጉምንም ፡ እንደሚበሩ ፡ ወፎች ፡ ይበትነዋል ፡
አወራረዱም ፡ እንደ ፡ አንበጣ ፡ አወራረድ ፡ ነው ።
ያነጣጡም ፡ መልክ ፡ ለዓይን ፡ ድንቅ ፡ ነው ፡ በረ ፲፰
ድን ፡ እንደ ፡ ጨው ፡ ይቀላቅላታልና ፡ ዝናምነ
ቱም ፡ ለልብ ፡ ድንቅ ፡ ነው ።
ጉሙንም ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ይበትነዋል ፡ ውር ፲፱
ጭም ፡ ከረጋ ፡ በኋላ ፡ ሸሮ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እንደ ፡
ብርሌ ፡ ስባሪ ፡ ብልጭ ፡ ይላል ።
የቀዘቀዘ ፡ የምሥራቅ ፡ ነፋስም ፡ ይነፍሳል ፡ ፳
ውርጭም ፡ በውኃ ፡ ላይ ፡ ይረጋል ፡ በውኃው ፡
አዟሪ ፡ ላይ ፡ ይቆማል ፡ እንደ ፡ ብረት ፡ ልብስም ፡
በውኃ ፡ ላይ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፡ ውኃይቱንም ፡
ይሸፍናታል ።
ተራራውን ፡ ይበላል ፡ ምድረ ፡ በዳውንም ፡ ያቃ ፳፩
ጥላል ፡ ሥሩንም ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ ያደርቀዋል ።

፳፪፡ የሰው ፡ ሁሉ ፡ ሕይወቱ ፡ ዝናም ፡ ፈጥኖ ፡ ቢዘ
ንም ፡ ነው ፡ ዝናምም ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ በወረደ፡
ጊዜ ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ።
፳፫፡ በእግዚአብሔር ፡ ምክር ፡ ውኃው ፡ ይደርቃል፡
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ኢያሱ ፡ በሐይን ፡ አቆመ ።
፳፬፡ በባሕርም ፡ የሚሄዱ ፡ ሰዎች ፡ መከራዋን ፡ ይና
ገራሉ ፡ እኛም ፡ ሰምተን ፡ እናደንቃለን ።
፳፭፡ በዚያም ፡ ሥራው ፡ ፈጽሞ ፡ ድንቅ ፡ ነው ።
ክብትንም ፡ መግዛት ፡ በየወገኑ ፡ ነው ።
፳፮፡ በጎ ፡ መንዝ ፡ አድርጎ ፡ ሊቀበለው ፡ ከነሳቸውም ፡
መሥዋዕት ፡ ይሠዋለታል ፡ በቃሉም ፡ ሁሉ ፡
ይደረጋል ።
፳፯፡ ብዙ ፡ ነገርን ፡ እንናገራለን ፡ የነገሩ ፡ መጨረሻ፡
እሱ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ መጨ
ረስ ፡ አንችልም ።
፳፰፡ ከፍጥረቱ ፡ ሁሉ ፡ እሱ ፡ ይበልጣልና ፡ እሱን ፡
ማመስገን ፡ ምን ፡ ያህል ፡ እንችላለን ።
፳፱፡ እግዚአብሔር ፡ ልው ፡ ነው ፡ የሚያስፈራ ፡
ነው ፡ ይልቁንም ፡ ገናንነቱም ፡ ያስፈራል ፡ ኃይ
ሉም ፡ ድንቅ ፡ ነው ።
፴፡ ጨርሳችሁ ፡ ማመስገንን ፡ አትጠነቀቁምና ፡
ምንም ፡ ብትጠነቀቁ ፡ የተቻላችሁን ፡ ያህል ፡
እግዚአብሔርን ፡ አመስግኑት ፡ አግኑት ። ዳግ
መኛም ፡ ከዚህ ፡ ሁሉ ፡ ይበልጣል ፡ በፍጹም ፡
እውቀታችሁም ፡ አግኑት ፡ አትደርሱበትምና ፡
ምንም ፡ ብትደርሱበት ፡ እሱን ፡ ማመስገንን ፡
ቻል ፡ አትበሉ ።
፴፩፡ አይቶ ፡ የሚነግረን ፡ ማነው ፡ በገናንነቱስ ፡ ልክ ፡
ማን ፡ ያገነዋል ።
፴፪፡ የማይታየው ፡ ከዚህ ፡ የሚበልጠው ፡ ፍጥረቱ ፡
ብዙ ፡ ነው ፡ ያየነው ፡ ፍጥረቱ ፡ ግን ፡ ጥቂት ፡
ብቻ ፡ ነው ።
፴፫፡ እግዚአብሔር ፡ ሁሉን ፡ ፈጥሯልና ፡ ለደጋጎች ፡
ሰዎች ፡ ጥበብን ፡ ሰጣቸው ።

ምዕራፍ ፡ ፵፬ ።

፩፡ የከበሩ ፡ ሰዎችን ፡ የጥበብን ፡ ምስጋና ፡ እና
መስግናቸው ፡ እግዚአብሔር ፡ ብዙ ፡ ክብር ፡
ሰጥቷቸዋልና ።
፪፡ ከተወለዱም ፡ ጀምሮ ፡ አግኗቸዋልና ፡ አባቶቻ
ችንንም ፡ በዘመናቸው ፡ እናመስግናቸው ።
፫፡ በኃይላቸው ፡ ስማቸውን ፡ ያስጠሩ ፡ ሰዎችም ፡
በመንግሥታቸው ፡ ገዙ ፡ በጥበባቸው ፡ የሚመ
ክሩ ፡ ትንቢትንም ፡ የሚናገሩ ፡ ነቢያት ፡ ደጋ
ጎች ፡ ናቸው ፡ እናመስግናቸው ።
፬፡ የአሕዛብም ፡ ነገሥታት ፡ በሰልፋቸው ፡ ደጋ
ጎች ፡ ናቸው ፡ እናመስግናቸው ፡ የሕዝቡም ፡
ጸሐፊዎች ፡ በጥበባቸው ፡ በልባቸውም ፡ ባለ ፡
በቃላቸው ፡ ጥበብ ፡ ደጋጎች ፡ ናቸው ፡ እናመ
ስግናቸው ።
፭፡ ምስጋናንና ፡ ያማረ ፡ መሰንቆን ፡ የሚፈልጉ ፡ በሕ
ፀግን ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ አድርገው ፡ የሚያመሰግኑ፡
ሴዋውያንም ፡ ደጋጎች ፡ ናቸው ፡ እናመስግ
ናቸው ።

ባለጸጎች ፡ የሆኑ ፡ ገንዘባቸው ፡ የሚበቃቸው ፡ ፮፡
በቤታቸው ፡ በሕይወት ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ደጋ
ጎች ፡ ናቸው ፡ እናመስግናቸው ።
እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ በዘመናቸው ፡ የከበሩ ፡ በሕይ ፯፡
ወታቸው ፡ የተዘጋጁ ፡ ናቸው ፡ እናመስግና
ቸው ።
ከነሳቸውም ፡ እሱን ፡ የሚናገሩት ፡ የከበረ፡ ፰፡
ስምንም ፡ የተዉ ፡ አሉ ።
የሚያስባቸው ፡ የሌለ ፡ የጠፉም ፡ ተፈጥረውም፡ ፱፡
እንዳልተፈጠሩ ፡ የሆኑ ፡ ተወልደውም ፡ ወዳለ
መወለድ ፡ የተመለሱ ፡ አሉ ፡ ልጆቻቸውም ፡
ከነሱ ፡ ጋራ ፡ እንደነሳቸው ፡ ጠፉ ።
በልብ ፡ ሥላሴ ፡ የተጻፉ ፡ ጽድቃቸው ፡ ያልተዘ ፲፡
ነጋችባቸው ።
ያማረች ፡ ርስታቸውም ፡ ከልጆቻቸው ፡ ጋራ ፡ ፲፩፡
ለዘለዓለም ፡ ጸንታ ፡ የምትኖር ፡ እነዚህ ፡ ሰዎች ፡
ግን ፡ ደጋጎች ፡ ናቸው ፡ እናመስግናቸው ።
ልጆቻቸውም ፡ በሥራቸው ፡ ጸንተው ፡ ይኖ ፲፪፡
ራሉ ።
ክብራቸውም ፡ አያልቅም ። ፲፫፡
ሥጋቸውም ፡ በተድላ ፡ በደስታ ፡ ተቀበረ ፡ ስማ ፲፬፡
ቸውም ፡ ለዘለዓለም ፡ ጸንታ ፡ ትኖራለች ።
አሕዛብም ፡ ጥበባቸውን ፡ ይናገራሉ ፡ በአሕዛ ፲፭፡
ብም ፡ ሸንጎ ፡ ያመሰግኗቸዋል ።
ሄኖክ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ደስ ፡ አሰኘው ፡ እግ ፲፮፡
ዚአብሔርም ፡ እሱን ፡ ከሞት ፡ ሠወረው ፡ ንስሐ ፡
ይገቡ ፡ ዘንድ ፡ ንስሐ ፡ ለሚገቡ ፡ ሰዎች ፡ አብ
ነት ፡ ሆነ ።
ኖኅም ፡ በውነት ፡ ፍጹም ፡ ሆኖ ፡ ተገኘ ፡ በጥፋ ፲፯፡
ትም ፡ ዘመን ፡ እሱ ፡ ለሰው ፡ ምግብ ፡ ሆነ ፡ የጥ
ፋትም ፡ ውኃ ፡ በወረደ ፡ ጊዜ ፡ እሱ ፡ ለዚህ ፡
ዘር ፡ ሆኖ ፡ ቀረ ።
የጥፋት ፡ ውኃ ፡ ሰውን ፡ ሁሉ ፡ እንዳያጠፋው ፡ ፲፰፡
እግዚአብሔር ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ ለዘለዓለሙ ፡ መሐ
ላን ፡ ተማማለ ።
የአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ አባት ፡ አብርሃም ፡ ደግ ፡ ነው ፡ ፲፱፡
እናመስግነው ፡ የከበረ ፡ ሕጉን ፡ የጠበቀ ፡ እን
ደሱ ፡ ያለ ፡ ሰውም ፡ አልተገኘ ።
እግዚአብሔር ፡ በሰውነቱ ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ ተማ ፳፡
ማለ ፡ አብርሃምም ፡ የእግዚብሔርን ፡ ሕግ ፡
ጠበቀ ፡ በፈተነውም ፡ ጊዜ ፡ የታመነ ፡ ሆኖ ፡
ተገኘ ።
አሕዛብ ፡ በልጆቹ ፡ ይከብሩ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ፳፩፡
ባሕር ፡ አሸዋም ፡ ያበዛቸው ፡ ዘንድ ፡ ልጆ
ቹም ፡ እንደ ፡ ሰማይ ፡ ከከብ ፡ ይበዙ ፡ ዘንድ ፡
ከባሕር ፡ እስከ ፡ ባሕርም ፡ ያወርሳቸው ፡ ዘንድ ፡
ከውቅያኖስም ፡ እስከ ፡ አድማስ ፡ ድረስ ፡ ያወር
ሳቸው ፡ ዘንድ ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ በመሐላ ፡ ቃል ፡
ኪዳን ፡ አጸናለት ።
ለይስሐቅም ፡ ስለ ፡ አባቱ ፡ ስለ ፡ አብርሃም ፡ ደግ ፳፪፡
ነት ፡ እንደሱ ፡ ቃል ፡ ኪዳንን ፡ አጸናለት ፡ በረከ
ትም ፡ ለሰው ፡ ሥራት ፡ ሆና ፡ ጸናች ።
በያዕቆብ ፡ ሰውነት ፡ አደረች ፡ በረከቱም ፡ ተገ ፳፫፡
ለጠችለት ፡ እሷንም ፡ ርስት ፡ አድርጎ ፡ ሰጠው ፡

ርስታቸውንም ፡ እየወገናቸው ፡ ለየላቸው ፡
ላሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ነገድም ፡ ርስታቸውን ፡ ከፈለላ
ቸው ።
፳፬ የክብሩ ፡ በሰውም ፡ ሁሉ ፡ ዘንድ ፡ መወደድን ፡
ያገኙ ፡ በሰውና ፡ በእግዚአብሔርም ፡ ዘንድ ፡ የተ
ወደዱ ፡ ደጋጎች ፡ ሰዎችን ፡ በነሳቸው ፡ አስነሣ ።

ምዕራፍ ፡ ፵፭ ።

፩ ስም ፡ አጠራሩ ፡ የከበረ ፡ የመላእክትም ፡ ብር
ሃን ፡ መልኩና ፡ ስም ፡ አጠራሩ ፡ የሆነ ፡ ሙሴ ፡
ደግ ፡ ነው ፡ እናመሰግነው ።
፪ አገነነው ፡ በጠላቶቹም ፡ ላይ ፡ የሚያስፈራ ፡
ሆነ ።
፫ በቃሉም ፡ ተአምራት ፡ አደረገ ፡ በነገሥታቱም ፡
ፊት ፡ ተመሰገነ ፡ ስለ ፡ ወገኖቹም ፡ አዘዘው ፡
ብርሃኑንም ፡ አሳየው ።
፬ ስለ ፡ የዋህነቱና ፡ ስለ ፡ ሃይማኖቱም ፡ አከበረው ፡
ከሰውም ፡ ሁሉ ፡ እሱን ፡ መረጠው ።
፭ ወደ ፡ ብርሃን ፡ መጋረጃ ፡ አግብቶ ፡ ቃሉንም ፡
አሰማው ፡ ትእዛዙንም ፡ በፊቱ ፡ ሰጠው ፡ ለሁ
ለቱ ፡ ነገድ ፡ አምልኮቱን ፡ ላሥሩ ፡ ነገድ ፡ ዘጠ
ኙን ፡ ሕግጋት ፡ ያስተምራቸው ፡ ዘንድ ፡ የእሬ
ትንም ፡ ሕግ ፡ አስተማረው ።
፮ ከሌዊ ፡ ወገን ፡ የተወለደ ፡ ታላቅ ፡ ወንድሙ ፡
አሮንም ፡ እንደሱ ፡ የከበረ ፡ ነው ፡ እናመስ
ግነው ።
፯ ፈጣሪውም ፡ ዘለዓለም ፡ ጸንቶ ፡ የሚኖር ፡ ሕግ ፡
አሪት ፡ አጸናለት ፡ ሕዝቡ ፡ የለዩት ፡ አሥራቱ
ንም ፡ ሰጠው ፡ በማረ ፡ ጌጥም ፡ አስደነቀው ፡ የክ
ብር ፡ ልብስንም ፡ አለበሰው ።
፰ በሁሉም ፡ ዘንድ ፡ አስመከው ፡ መቅሠፍት ፡ በታ
ዘዘበት ፡ ወራትም ፡ አጸናው ፡ እጀ ፡ ሰፊና ፡ እጀ ፡
ጠባብን ፡ ኤፉድንም ፡ አለበሰው ።
፱ በዙሪያውም ፡ ብዙ ፡ የሆነ ፡ የወርቅ ፡ ጸናጽልና ፡
አበባ ፡ አለ ፡ በእግሩም ፡ በረገጠ ፡ ጊዜ ፡ የመር
ገፉ ፡ ድምፅ ፡ ይሰማ ፡ ነበር ፡ ጮሆ ፡ የተናገረ
ውም ፡ ነገር ፡ ቋም ፡ ነገር ፡ ይሆን ፡ ነበር ፡ ለልጆ
ቻቸውና ፡ ለወገኑም ፡ መታሰቢያ ፡ ሆነ ።
፲ የተለየ ፡ ሰማያዊ ፡ ሐር ፡ ያለበት ፡ አራት ፡ ኅብር ፡
አምስተኛ ፡ ወርቀ ፡ ዘቦ ፡ ያለበት ፡ በነጭ ፡ ሐር ፡
የተሠራ ፡ ልብስንም ፡ በሚገባና ፡ በውነት ፡ ነገር ፡
የተሠራ ፡ የሉግዮ ፡ ልብስንም ፡ አለበሰው ።
፲፩ የነጭ ፡ ሐር ፡ የሚሆን ፡ ፈትሉ ፡ እጥፍ ፡ የሆነ ፡
የብልሀ ፡ ሥራ ፡ የሚሆን ፡ ዋጋው ፡ ድንቅ ፡ የሆነ ፡
ዕንቍም ፡ ያለበት ፡ የማኅተምም ፡ ቅርጽ ፡ ያለ
በት ፡ ልብስን ፡ በልብስ ፡ ላይ ፡ አለበሰው ፡ እጀ ፡
ጠባቡም ፡ በወርቅ ፡ የተሠራ ፡ ነው ፡ በየወገና
ቸው ፡ መታሰቢያ ፡ ሊሆን ፡ በ፲፪ቱ ፡ ነገደ ፡ እስ
ራኤል ፡ ልጆች ፡ ቍጥር ፡ ልክ ፡ የተጻፈ ፡ ነው ።
፲፪ በማኅተም ፡ መልክ ፡ አምሳል ፡ በተሠራ ፡ የተ
ሠራ ፡ የወርቅ ፡ ቀጸላ ፡ በዝግራ ፡ መጠምጠሚ
ያው ፡ ላይ ፡ አደረገለት ፡ የተለየ ፡ የክብሩ ፡ መመ
ኪያ ፡ የሚሆን ፡ ታምራት ፡ የሚያደርግበት ፡
ሥራ ፡ የሚሆን ፡ ጌጡ ፡ ለዓይን ፡ የተወደደ ፡
የሆነ ፡ ጌጡ ፡ ፈጽሞ ፡ ያማረ ፡ የሆነ ፡ የወርቅ ፡
መጠምጠሚያን ፡ በዝግራ ፡ መጠምጠሚያው ፡
ላይ ፡ አደረገለት ።
ከሱ ፡ አስቀድሞ ፡ ከሱም ፡ በኋላ ፡ እንደሱ ፡ ፲፫
ልብስ ፡ ያለ ፡ ልብስ ፡ አልተሠራም ፡ ከልጆቹ ፡
ብቻ ፡ በቀር ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ከዘመዶቹም ፡ በቀር ፡
እንደሱ ፡ የለበሰ ፡ የለም ።
ሁለጊዜ ፡ መሥዋዕት ፡ ይሠዉለት ፡ ዘንድ ፡ ዳግ ፲፬
መኛም ፡ እየነጋ ፡ የማታና ፡ የጧት ፡ መሥዋ
ዕት ፡ ይሠዉለት ፡ ዘንድ ፡ ልጆቹ ፡ ብቻ ፡ ዘመ
ዶቹም ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ለበሱ ፡ እንጂ ፡ እንደሱ ፡
የለበሰ ፡ የለም ።
ሙሴ ፡ እጆቻቸውን ፡ ቀባላቸው ፡ የተለየ ፡ ዘይት ፲፭
ንም ፡ ቀባው ፡ ለዘለዓለሙም ፡ ሕግ ፡ ሆነው ፡
ይገዙለት ፡ ዘንድ ፡ አገልጋዮችም ፡ ይሆኑት ፡
ዘንድ ፡ ስሙን ፡ ጠርተው ፡ ሕዝቡንም ፡ ይባር
ኳቸው ፡ ዘንድ ፡ ሰማይ ፡ ጸንቶ ፡ በሚኖርበት ፡
ዘመን ፡ ልክ ፡ ለልጆቹም ፡ ሕግ ፡ ሆናቸው ።
ለእግዚአብሔር ፡ መሥዋዕት ፡ ይሠዋ ፡ ዘንድ ፡ ፲፮
የበጎ ፡ መዓዛ ፡ መታሰቢያ ፡ ሊሆን ፡ ዕጣንንም ፡
ያጥን ፡ ዘንድ ፡ ለወገኖቹም ፡ ኃጢአታቸውን ፡
ያስተሠርይላቸው ፡ ዘንድ ፡ ከሰዎቹ ፡ ሁሉ ፡
እሱን ፡ መረጠ ።
ትእዛዙን ፡ አስተማረው ፡ ለሁለቱ ፡ ነገድ ፡ አም ፲፯
ልኮቱን ፡ ያስተምራቸው ፡ ዘንድ ፡ ለዓሥሩም ፲
ነገድ ፡ ዘጠኙን ፡ ሕግጋት ፡ ያስተምራቸው ፡
ዘንድ ፡ ዘጠኙን ፡ ሕግጋትና ፡ አምልምኮቱን ፡
ሠራለት ።
ልዩ ፡ የሆኑ ፡ ሰዎች ፡ ተከራከሩት ፡ የአቤሮንና ፡ ፲፰
የዳታን ፡ ወገኖች ፡ የሚሆኑ ፡ ሰዎች ፡ የነቆሬም ፡
ሠራዊቶች ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ቀኑበት ፡ በጥፋ
ትና ፡ በመቅሠፍትም ፡ ሞቱ ።
እግዚአብሔርም ፡ አይተው ፡ ደስ ፡ አላሰኙትም ፡ ፲፱
ተቈጥቶም ፡ አጠፋቸው ፡ በለሳቸውም ፡ ድንቅ ፡
ታምራት ፡ አደረገ ፡ በእሳትም ፡ አቃጠላቸው ።
ለአሮንም ፡ በክብር ፡ ላይ ፡ ክብር ፡ ጨመረለት ፡ ፳
ከእህላቸው ፡ የለዩት ፡ አሥራቱንም ፡ ሰጠው ፡
የወገኖቹን ፡ ምድር ፡ እንዳይከፈሉ ፡ ለሱ ፡ የሰ
ጠውን ፡ ለልጆቹም ፡ የሰጣቸውን ።
የእግዚአብሔርን ፡ መሥዋዕት ፡ ይበሉ ፡ ዘንድ ፡ ፳፩
የሚያጠግባቸው ፡ አሥራቱን ፡ አስቀድሞ ፡ ሠራ
ላቸው ።
እድልህ ፡ ርስትህ ፡ አሥራቱ ፡ ነው ፡ ብሎታ ፳፪
ልና ፡ ከሕዝቡ ፡ ጋራ ፡ ርስትን ፡ አልወረሰም ።
ለእግዚአብሔር ፡ አምልኮት ፡ ቀንቷልና ፡ ወገ ፳፫
ኖቹን ፡ ለማስተማር ፡ ሾሞታልና ፡ ሹመቱ ፡ ሦስ
ተኛ ፡ የሚሆን ፡ የአልዓዛር ፡ ልጅ ፡ ፊንሐስም ፡
ደግ ፡ ነው ፡ እናመስግነው ፡ በልቡናው ፡ ቸር
ነት ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ የተነሣ ፡ ለእስ
ራኤል ፡ ተገለጠ ።
በሙሴና ፡ በአሮን ፡ ሥራት ፡ ጸንቶ ፡ ሕዝቡን ፡ ፳፬
ያስተምራቸው ፡ ዘንድ ፡ ለልጆቹና ፡ ለሱም ፡
ለዘለዓለም ፡ ጸንቶ ፡ የሚኖር ፡ ደግ ፡ ክህነት ፡ ገን
ዘብ ፡ ይሆናቸው ፡ ዘንድ ።

፳፭ ከነገደ ፡ ይሁዳ ፡ ለተወለደ ፡ ለዳዊት ፡ ልጅም ፡
ጌጥ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ በሕጉ ፡ ጸንቶ ፡ የሚኖር ፡
የልጁም ፡ መንግሥትም ፡ እድል ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡
ስለዚህ ፡ ነገር ፡ የፍቅር ፡ አንድነት ፡ መሐላን ፡
አጸናለት ።
፳፮ ከልቡናቸው ፡ ጥልቅ ፡ ብሎ ፡ የሚገባ ፡ ጥበብን ፡
ያስተምራቸው ፡ ዘንድ ፡ በዘመናቸው ፡ ሁሉ ፡
ክብራቸውና ፡ በረከታቸው ፡ እንዳይጠፋባቸው ፡
ወገኖቹንም ፡ በውነት ፡ ይገዟቸው ፡ ዘንድ ፡ ከል
ጆቹ ፡ ጋራ ፡ ለሱ ፡ ክህነት ፡ ርስቱ ፡ ነው ።

ምዕራፍ ፡ ፵፮ ።

፩ የነዌ ፡ ልጅ ፡ ኢያሱም ፡ በሰልፍ ፡ ጊዜ ፡ አር
በኛ ፡ ነው ፡ እናመስግነው ። ከሙሴም ፡ ቀጥሎ ፡
ትንቢት ፡ ተናገረ ፡ እንደ ፡ ስሙም ፡ የገነነ ፡ ሆነ ፡
ወዳጆቹንም ፡ ከመከራ ፡ አዳናቸው ፡ ለእስራ
ኤል ፡ ምድራቸውን ፡ ያወርሳቸው ፡ ዘንድ ፡ ጠላ
ቶቻቸውንም ፡ ተበቅሎ ፡ አጠፋ ።
፪ ጋሻውን ፡ በእጁ ፡ ይዞ ፡ በጠቀሰ ፡ ጊዜ ፡ በገራ
ቸውም ፡ ላይ ፡ ጦሩን ፡ በወረወረ ፡ ጊዜ ፡ ተመ
ሰገነ ።
፫ ከሱ ፡ አስቀድሞ ፡ እንደሱ ፡ የሆነ ፡ ማነው ፡ እሱ ፡
እግዚአብሔርም ፡ ጠላታቸውን ፡ አጠፋላቸው ።
፬ ኢያሱም ፡ ደግ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ይታወቅ ፡ ዘንድ ፡
ፀሐይ ፡ በቃሉ ፡ ያቆመ ፡ አይደለምን ። አንዲ
ቱስ ፡ ቀን ፡ ሁለት ፡ ቀን ፡ የሆነች ፡ አይደለምን ።
፭ በዙሪያው ፡ ያሉ ፡ ጠላቶቹ ፡ በስጨነቁት ፡ ጊዜ ፡
ገናና ፡ ኃይለኛ ፡ የሚሆን ፡ እግዚአብሔርን ፡
ለመነው ፡ የበረድ ፡ ደንጊያ ፡ አዝንምልኝ ፡ ጽኑ ፡
ኃይልም ፡ አድርግልኝ ፡ ብሎ ፡ ገናና ፡ እግዚአ
ብሔርን ፡ ለመነው ።
፮ በተጣሏቸው ፡ በአሕዛብም ፡ ላይ ፡ የበረድ ፡ ደን
ጊያ ፡ ያዘነመ ፡ የሚያጠፋላቸው ፡ እሱ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ነውና ፡ ቀጥሎ ፡ ቀጥሎም ፡ ኃይሉን ፡
አድርጎላቸዋልና ፡ ሕዝቡ ፡ ኃይሉን ፡ ያውቁ ፡
ዘንድ ፡ የተዋጓቸው ፡ ጠላቶቻቸውን ፡ በገደል ፡
መካከል ፡ አጠፋላቸው ።
፯ በሙሴም ፡ ዘመን ፡ ይቅርታውን ፡ አደረገላቸው ፡
የዮፎኒ ፡ ልጅ ፡ ካሌብና ፡ እሱ ፡ በጠላት ፡ ፊት ፡
ተከራከሩ ፡ ሕዝቡንም ፡ በደልን ፡ ከለከሏቸው ፡
ክፉ ፡ አንጐርጓሮንም ፡ አስተዋቸው ።
፰ ከስሳው ፡ እልፍ ፡ አርበኞች ፡ የዳኑ ፡ እነሳቸው ፡
ሁለቱ ፡ ብቻ ፡ ናቸው ፡ ማርና ፡ ወተት ፡ ወደም
ታስገኝ ፡ ወደ ፡ ከነዓንም ፡ ገቡ ። (ተድላ ፡ ደስታ ፡)
፱ እግዚአብሔርም ፡ ለካሌብ ፡ ኃይልን ፡ ሰጠው ፡
እስኪያረጅም ፡ ድረስ ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ በረድኤት ፡
ኖረ ፡ ወደ ፡ ኬብሮንም ፡ አወጣው ፡ የእስራኤል ፡
ልጆች ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ መከተል ፡
ያማረ ፡ የተወደደ ።
፲ እንደ ፡ ሆነ ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ፡ ልጆቹም ፡ ርስታቸ
ውን ፡ ተካፈሉ ።
፲፩ በየስማቸው ፡ የተጠሩ ፡ የእስራኤል ፡ ገዢዎች ፡
ልቡናቸውም ፡ በኃጢአት ፡ ያልሰሰነ ፡ ሰዎች ፡
ሁሉ ፡ እግዚአብሔርንም ፡ በአምልኮ ፡ ያልተ
ዉ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ስም ፡ አጠራራቸው ፡ የከ
በረ ፡ ይሁን ።
በኖሩበትም ፡ አገር ፡ ሰውነታቸውን ፡ ደስ ፡ ይለ ፲፪
ዋል ፡ ልጆቻቸውም ፡ ይበረክቱ ፡ ይከብራሉ ።
ሳሙኤልም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የተወ ፲፫
ደደ ፡ ነው ፡ እናመስግነው ፡ ትንቢት ፡ የሚና
ገር ፡ ነው ፡ ቀብቶም ፡ ለሕዝቡ ፡ ንጉሥን ፡ ያነ
ግሥል ።
በእግዚአብሔርም ፡ ሕግ ፡ ጸንቶ ፡ ሳኦልን ፡ ቀብ ፡ ፲፬
እግዚአብሔርም ፡ ያዕቆብን ፡ ይቅር ፡ አለው ።
አምኖ ፡ የተናገረውም ፡ ትንቢት ፡ ጸና ፡ በቃ ፲፭
ሉም ፡ እውነተኛ ፡ ራዕይ ፡ ተገለጠ ።
ጠላቶቹ ፡ በስጨነቁት ፡ ጊዜ ፡ የበግም ፡ ጠቦት ፡ ፲፮
ሲሠዋ ፡ በከበቡት ፡ ጊዜ ፡ ኃይለኛ ፡ የሆነ ፡ እግ
ዚአብሔርን ፡ ለመነው ።
እግዚአብሔርም ፡ በሰማይ ፡ ሆኖ ፡ ድምጥ ፡ ፲፯
አሰማ ፡ በጸለየውም ፡ ጸሎት ፡ ነገር ፡ የሚያስ
ፈራ ፡ መብረቅ ፡ ተሰማ ።
የፍልስጥኤምና ፡ የጢሮስንም ፡ ነገሥታት ፡ ፲፰
ሁሉ ፡ አጠፋቸው ።
የሚሞትበትም ፡ ቀን ፡ ሳይደርስ ፡ ለእግዚአብ ፲፱
ሔር ፡ ቃል ፡ አሰማው ፡ ከገንዘባቸው ፡ እስከ ፡
ጫማ ፡ ድረስ ፡ ከነሳቸው ፡ እንዳልወሰደ ፡ ለሳኦ
ልም ፡ ቃል ፡ አሰማው ፡ ከነሳቸውም ፡ የነቀፈው ፡
የለም ።
ከሞተም ፡ በኋላ ፡ ትንቢት ፡ ተናገረ ፡ የንጉሡ ፳
ንም ፡ ሞት ፡ ተናገረ ፡ ከመቃብርም ፡ ተነሥቶ ፡
ነገር ፡ ተናገረ ፡ ትንቢትም ፡ በመናገሩ ፡ የሕዝ
ቡን ፡ ኃጢአት ፡ ሳአልን ፡ አጠፋ ።

ምዕራፍ ፡ ፵፯ ።

ከሱም ፡ በኋላ ፡ ተነሥቶ ፡ ናታን ፡ በዳዊት ፡ ፩
ዘመን ፡ ትንቢት ፡ ተናገረ ።
ድኅነት ፡ የሚደረግበትን ፡ የመሥዋዕትን ፡ ስብ ፡ ፪
እንዲለዩ ፡ እንደዚሁ ፡ ዳዊት ፡ ከእስራኤል ፡
ልጆች ፡ የተለየ ፡ ሆነ ።
በሱም ፡ ዘንድ ፡ አንበሳ ፡ እንደ ፡ ፍየል ፡ ጠቦት ፡ ፫
ግስላም ፡ እንደ ፡ በግ ፡ ጠቦት ፡ ሆነ ።
ዳዊትማ ፡ አርበኛ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ይታወቅ ፡ ዘንድ ፡ ፬
በሕፃንነቱ ፡ አርበኛ ፡ ጐልያድን ፡ የገደለ ፡ አይ
ደለምን ፡ እጁንስ ፡ አንሥቶ ፡ ደንጊያ ፡ በወረ
ወረ ፡ ጊዜ ፡ ጐልያድን ፡ ግንባሩን ፡ የመታው ፡
ናላውንም ፡ የበጠበጠው ፡ አይደለምን ፡ ሕዝቡ
ንስ ፡ መሰደባቸውን ፡ ያስተዋቸው ፡ አይደለ
ምን ።
ገናና ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለምኖታልና ፡ በሰልፍ ፡ ፭
ኃይለኛ ፡ ጐልያድን ፡ ይገድል ፡ ዘንድ ፡ የወገኖ
ቹንም ፡ ሥልጣን ፡ ያጸና ፡ ዘንድ ፡ በቀኝ ፡ እጁ ፡
ኃይልን ፡ አሳደረበት ።
ዘፋኞቹም ፡ ዳዊትን ፡ እልፍ ፡ ገዳይ ፡ አሉት ፡ ፮
በእግዚአብሔርም ፡ ምስጋና ፡ አመሰገኑት ፡ በጌ
ትነትም ፡ ዘውድ ፡ ተቀዳጀ ።
በዙሪያው ፡ ያሉ ፡ ጠላቶቹንም ፡ አጠፋቸው ፡ ፯
የፍልስጥኤምንም ፡ ሰዎች ፡ አጐሰቈላቸው ፡

ሥልጣናቸውንም ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ አጠ
ፋው ።
፰፤ በሠራው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያም
ነ፡በት ፡ ነበር ፡ በእግዚአብሔርም ፡ ጌትነት ፡
ቃል ፡ ያምን ፡ ነበር ፡ በሥራውም ፡ ሁሉ ፡ አመ
ሰገነው ፡ ፈጣሪውንም ፡ አመሰገነው ፡ ወደደው ።
፱፤ በመሠዊያውም ፡ ካህናትን ፡ ሾመ ፡ የቃላቸ
ውም ፡ ዜማ ፡ ያማረ ፡ የተወደደ ፡ ነው ።
፲፤ ደግ ፡ በዓልንም ፡ አደረገ ፡ እግዚአብሔርም ፡
በዘመኑ ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ አሰኘው ፡ ክቡር ፡ ስሙ
ንም ፡ አመሰገነው ፡ ምስጋናውም ፡ ከነግህ ፡
ጀምሮ ፡ ይነገራል ።
፲፩፤ እግዚአብሔርም ፡ ኃጢአቱን ፡ አስተሠረየለት ፡
ሥልጣኑንም ፡ ለዘለዓለሙ ፡ አጸናለት ፡ የከበ
ረች ፡ መንግሥትንም ፡ ሰጠው ፡ የእስራኤል ፡
የሚከብሩበት ፡ ዙፋንንም ፡ ሰጠው ።
፲፪፤ ከሱም ፡ በኋላ ፡ አዋቂ ፡ የሆነ ፡ ልጁ ፡ ተተካለት ፡
ስለሱም ፡ ደግነት ፡ በተድላ ፡ በደስታ ፡ ኖረ ።
፲፫፤ ሰሎሞንም ፡ ፍቅር ፡ አንድነት ፡ በጸናበት ፡
ወራት ፡ ነገሠ ፡ እግዚአብሔርም ፡ በዙሪያው ፡
ካሉ ፡ ጠላቶቹ ፡ አሳረፈው ፡ በስሙ ፡ ቤት ፡ መን
ግሥትን ፡ ሠራ ፡ ዘለዓለም ፡ ጸንቶ ፡ የሚኖር ፡
ቤት ፡ መቅደስንም ፡ በስሙ ፡ አምኖ ፡ ሠራ ።
፲፬፤ ሰሎሞን ፡ ከሕፃንነትህ ፡ ጀምሮ ፡ ጥበብህ ፡ በዛ ፡
ጥበብህም ፡ እንደ ፡ ፈሳሽ ፡ ውሀ ፡ በሰው ፡ ልቡና ፡
መላች ።
፲፭፤ ዕውቀትም ፡ ሰውነትህን ፡ ሸፈነቻት ፡ ምሳሌህን ፡
የነገርህንም ፡ ትርጓሜ ፡ አበዛህ ።
፲፮፤ ስምህም ፡ እስከ ፡ ራቀ ፡ ደሴት ፡ ድረስ ፡ ተሰማ ፡
ዘመንህ ፡ ዘመነ ፡ ሰላም ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ በምሳሌ
ህና ፡ በምስጋናህ ፡ በነገርህም ፡ ወደዱህ ።
፲፯፤ የእስራኤል ፡ ፈጣሪ ፡ በተባለ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ስም ፡ ጸንተህ ፡ ከተናገርከው ፡ ትርጓሜ ፡ የተ
ነሣ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ አደነቁህ ።
፲፰፤ ወርቁንም ፡ እንደ ፡ እርሳስ ፡ አደለብከው ፡ ብር
ንም ፡ እንደ ፡ ቀልቅል ፡ መላኸው ።
፲፱፤ ሴቶችም ፡ ልቡናህን ፡ ለወጡት ፡ በግዛፍህም ፡
ጸናህ ።
፳፤ መንግሥትህን ፡ አስነቀፍህ ፡ ልጆችህንም ፡ ኃጢ
አተኞች ፡ አደረግህ ፡ በልጆችህም ፡ መቅሠፍ
ትና ፡ ጥፋት ፡ አመጣህ ፡ ሰሎሞን ፡ ስንፍናህ ፡
አስደነገጠኝ ።
፳፩፤ ከግዛግዝህም ፡ ተለየህ ፡ ከሥሩ ፡ ነገድም ፡ አመ
ፀኛ ፡ መንግሥትም ፡ ተገኘች ።
፳፪፤ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ ቸርነቱን ፡ አልተወም ፡
ፍጥረቱንም ፡ አላጠፋም ፡ የደጋግ ፡ ሰዎች ፡ ልጆ
ችንም ፡ አላጠፋም ፡ የሚወዱትንም ፡ ሰዎች ፡
ልጆች ፡ በሞት ፡ አላራቀም ፡ ለያዕቆብ ፡ ልጅ ፡
ሰጠው ፡ ለዳዊትም ፡ ከሱ ፡ የተወለደ ፡ ልጅ ፡
ሰጠው ።
፳፫፤ ሰሎሞንም ፡ እንደ ፡ አባቶቹ ፡ ሞተ ፡ ከሱም ፡
በኋላ ፡ አእምሮ ፡ የሌለው ፡ ልጅን ፡ ለእስራኤል ፡
ተወ ። ይኸውም ፡ ወገኖቹን ፡ ያስወነጀላቸው ፡
ሮብዓም ፡ ነው ። እስራኤልን ፡ ያሳታቸው ፡ ኢዮ
ርብዓምም ፡ ከሱ ፡ ነው ፡ እንንቀፈው ፡ ለሥሩም ፡
ነገድ ፡ የኃጢአት ፡ ምክንያት ፡ አደረገ ።
ኃጢአታቸውም ፡ ፈጽሞ ፡ በዛ ፡ ከሀገራቸውም ፡ ፳፬፤
አስወጥቶ ፡ ሰደዳቸው ።
ፍዳቸውም ፡ እስክትደርስባቸው ፡ ድረስ ፡ ኃጢ ፳፭፤
አትን ፡ ሁሉ ፡ ሠሩት ።

ምዕራፍ ፡ ፵፰ ።

ነቢዩ ፡ ኤልያስም ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ በማስፈ ፩፤
ራት ፡ ተነሣ ፡ ቃሉም ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ ያቃጥላል ።
ረኃብንም ፡ አመጣባቸው ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ፪፤
ሕግ ፡ በመቅናቱም ፡ በሞት ፡ አሰነሣቸው ።
በእግዚአብሔርም ፡ ቃል ፡ ዝናምን ፡ ከለከለ ፡ ፫፤
ሰማይንም ፡ ዘጋው ፡ ከሰማይ ፡ እሳትን ፡ ሦስት ፡
ጊዜ ፡ አወረደ ።
ኤልያስ ፡ በተአምራትህ ፡ እንዴት ፡ ተመሰገንህ ፡ ፬፤
እንዳንተስ ፡ የተመካ ።
ከሞቱ ፡ ሰዎች ፡ ለይቶ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ፭፤
ሙትን ፡ ከመቃብር ፡ ያስነሣ ፡ ማነው ።
ነገሥታቱን ፡ በሞት ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ አወረ ፮፤
ዳቸው ፡ የከበሩ ፡ ነገሥታትንም ፡ ከዙፋናቸው ፡
እየገለበጠ ፡ ጣላቸው ።
በኮሬብና ፡ በደብረ ፡ ሲና ፡ የተሠራውን ፡ ሕግ ፡ ፯፤
ቢያፈርሱ ፡ መቻያ ፡ የሚያመጣ ፡ እሱ ፡ ነው ፡
ፍርድንም ፡ በቀልንም ፡ የሚያመጣ ፡ እሱ ፡ ነው ።
ነገሥታቱን ፡ የሚቀባቸው ፡ እሱ ፡ ነው ፡ ፍዳ ፰፤
ንም ፡ የሚያመጣባቸው ፡ እሱ ፡ ነው ፡ ነቢያትም ፡
እሱን ፡ ከመከተል ፡ ተመለሱ ።
በእሳት ፡ ፈረስና ፡ በእሳት ፡ ሠረገላ ፡ ወደ ፡ ፱፤
ሰማይ ፡ የወጣ ፡ እሱ ፡ ነው ።
ከመቅሠፍቱ ፡ አስቀድሞ ፡ የሚመጣውን ፡ ቍጣ ፡ ፲፤
ይመልስ ፡ ዘንድ ፡ ያባትንም ፡ ዕውቀት ፡ ወደ ፡
ልጆች ፡ ይመልስ ፡ ዘንድ ፡ የያዕቆብንም ፡ ወገ
ኖች ፡ ያጸናቸው ፡ ዘንድ ፡ በየጊዜው ፡ ፍርድን ፡
የሚጽፍ ፡ እሱ ፡ ነው ።
ኤልያስ ፡ የሚያውቁህ ፡ በፍቅርህም ፡ ያጌጡ ፡ ፲፩፤
ሰዎች ፡ የተደነቁ ፡ ናቸው ፡ እኛም ፡ ስላንተ ፡
ደግነት ፡ በሕይወት ፡ እንኖራለን ።
በእሳት ፡ ሠረገላ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ የወጣ ፡ ኤል ፲፪፤
ያስ ፡ ነው ፡ የኤልያስ ፡ ሀብት ፡ ያደረበት ፡ ኤል
ሳዕም ፡ ደግ ፡ ነው ፡ እናመስግነው ፡ በዘመኑም ፡
የሰርያ ፡ አለቆች ፡ አላስደነገጡትም ፡ ማንም ፡
ማን ፡ እሱን ፡ የቀማው ፡ የለም ።
ከነገሩም ፡ ሁሉ ፡ የተሠወረው ፡ የለም ፡ ከሞ ፲፫፤
ተም ፡ በኋላ ፡ ሬሳው ፡ ትንቢት ፡ ተናገረ ።
በሕይወቱም ፡ ሳለ ፡ ድንቅ ፡ ተአምራት ፡ አደረገ ፡ ፲፬፤
ከሞተም ፡ በኋላ ፡ ሥራው ፡ ድንቅ ፡ ነው ።
ከዚህም ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ ሕዝቡ ፡ ንስሐ ፡ አልገ ፲፭፤
ቡም ፡ ከገራቸውም ፡ እስኪማረኩ ፡ ድረስ ፡ ኃጢ
አታቸውን ፡ አልተዉም ፡ በሀገሩ ፡ ሁሉ ፡ ተበ
ተኑ ፡ ከሕዝቡም ፡ ጥቂት ፡ ሰዎች ፡ ቀሩ ፡ ከዳዊ
ትም ፡ ወገን ፡ ቀበሁ ።
ከነሳቸውም ፡ ደግ ፡ ሥራ ፡ የሠሩ ፡ አሉ ፡ ኃጢ ፲፮፤
አትንም ፡ ያበዙት ፡ አሉ ።

፲፯፤ ሕዝቅያስም ፡ አገሩን ፡ አጸና ፡ ደግ ፡ ነው ፡ እና
መስግነው ፡ ወደ ፡ ከተማውም ፡ መካከል ፡ ውኃ ፡
አገባ ፡ በብረትም ፡ አለቱን ፡ አለዘበ ፡ የውኃ ፡
ጕሬንም ፡ አስቈፈረ ።
፲፰፤ ሰናክሬምም ፡ በዘመኑ ፡ ዘመተ ፡ ራፋስቂስንም ፡
ላከው ፡ ወደሱም ፡ ሔዶ ፡ በኢየሩሳሌም ፡
እጁን ፡ አነሣ ፡ ታበየ ፡ አፉንም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡
አድርጎ ፡ ተናገረ ።
፲፱፤ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ልቡናቸው ፡ ደነገጠባቸው ፡
እጃቸውም ፡ ከመወርወር ፡ ደከመ ፡ እንደምት
ወልድ ፡ ሴትም ፡ ተጨነቁ ።
፳፤ ይቅር ፡ ባይ ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ለመኑ ፡ እደ፡
ቃላቸውን ፡ ወደሱ ፡ አነሡ ፡ የከበረ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ በሰማይ ፡ ሆኖ ፡ ልመናቸውን ፡ ሰማቸው ፡
በኢሳይያስ ፡ ጸሎትም ፡ አዳናቸው ።
፳፩፤ የፋርስንም ፡ ሠራዊት ፡ አጠፋ ፡ ቅዱስ ፡ ሚካኤ
ልም ፡ አጠፋቸው ።
፳፪፤ ሕዝቅያስ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ደስ ፡ የሚያሰኘው ፡
ሥራ ፡ ሠርቷልና ፡ ነቢዩ ፡ ኢሳይያስም ፡ እንዳ
ዘዘው ፡ ያባቱ ፡ የዳዊትንም ፡ ሥራት ፡ አጽንቷ
ልና ፡ ቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡ አጠፋቸው ። ኢሳይ
ያስ ፡ የታመነ ፡ ነው ፡ ራእዩም ፡ ደግ ፡ ነው ።
፳፫፤ ፀሐይም ፡ በዘመኑ ፡ ከመሔድ ፡ ተከለከለች ፡ ለሕ
ዝቅያስም ፡ ዘመን ፡ ጨመረለት ።
፳፬፤ በደግ ፡ ዕውቀትም ፡ የእስራኤልን ፡ መመለስ ፡
አየ ፡ ለኢየሩሳሌም ፡ የሚያለቅሱላት ፡ ሰዎች
ንም ፡ ደስ ፡ አሰኛቸው ።
፳፭፤ ለዘለዓለሙ ፡ የሚደረገውን ፡ የተሠወረውንም ፡
ሳይደረግ ፡ ተናገረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፱ ።

፩፤ መዓዛው ፡ እንደ ፡ ተወደደ ፡ ሽቱ ፡ በሰውም ፡
ሁሉ ፡ አፍ ፡ እንደሚጣፍጥ ፡ እንደ ፡ ማርም ፡
በመጠጥም ፡ ጊዜ ፡ ዘፈን ፡ ደስ ፡ እንደሚያሰኝ ፡
ስም ፡ አጠራሩ ፡ የጥበብ ፡ ስም ፡ አጠራር ፡ ኢዮ
ስያስም ፡ ደግ ፡ ነው ፡ እናመስግነው ።
፪፤ እሱስ ፡ የቀና ፡ ነው ፡ ሕዝቡን ፡ መለሳቸው ፡
የሚያጸይፍ ፡ ኃጢአትንም ፡ አራቀ ።
፫፤ ልቡናውንም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ አቀና ፡
በኃጢአተኞችም ፡ ሰዎች ፡ ዘመንም ፡ ጽድቅን ፡
አጸናት ።
፬፤ ኢዮስያስና ፡ ሕዝቅያስ ፡ ዳዊትም ፡ ብቻ ፡ ደጋግ ፡
ሰዎች ፡ ናቸው ፡ እናመስግናቸው ፡ እነዚያ ፡
ሁላቸው ፡ ግን ፡ ፈጽመው ፡ በደሉ ፡ የእግዚአ
ብሔርንም ፡ ሕግ ፡ አፈረሱ ፡ ሥልጣናቸውን ፡
ለባዕድ ፡ ሰው ፡ ሰጥተዋልና ።
፭፤ ጌትነታቸውንም ፡ ለሌላ ፡ ሰው ፡ ሰጥተዋልና ፡
የይሁዳ ፡ ነገሥታት ፡ ጠፉ ።
፮፤ ደግ ፡ የሆነች ፡ የከበረች ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ በእ
ሳት ፡ አቃጠሏት ፡ መከራ ፡ አጽንተውባታልና ፡
በነቢዩ ፡ በኤርምያስ ፡ ጸሎት ፡ ጐዳናዋን ፡
አጠፉ ።
፯፤ እሱ ፡ ግን ፡ መምህር ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ይነቅል ፡
ዘንድ ፡ ያጠፋም ፡ ዘንድ ፡ እንደዚሁ ፡ ይተክል ፡
ዘንድ ፡ ይሠራም ፡ ዘንድ ፡ በናቱ ፡ መኀፀን ፡ ተመ
ረጠ ።
ጌትነቱን ፡ ፈጽሞ ፡ ያየ ፡ ሕዝቅኤል ፡ ደግ ፡ ነው ፡ ፰፤
እናመስግነው ፡ እግዚአብሔርንም ፡ ኪሩቤል ፡
በተሸከሙት ፡ ሠረገላ ፡ ተቀምጦ ፡ አየው ።
ጠላቶቹንም ፡ በመዓት ፡ አሰባቸው ፡ የደጋጎች ፡ ፱፤
ሰዎች ፡ ሥራቸውን ፡ ግን ፡ በበጎ ፡ ሥራ ፡ አቀ
ናቸው ።
አሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ነቢያት ፡ በየበታቸው ፡ በረድ ፲፤
ኤት ፡ ታደሱ ፡ ያዕቆብንም ፡ ደስ ፡ አሰኘው ፡
ተስፋቸው ፡ በሚሆን ፡ ሃይማኖትም ፡ ከመከ
ራው ፡ አዳናቸው ።
ዘሩባቤልን ፡ እንዴት ፡ እናገነው ፡ ይሆን ፡ እንጃ ፡ ፲፩፤
እሱስ ፡ በቀኝ ፡ እጅ ፡ እንዳለ ፡ እንደ ፡ ኀትም ፡
ቀለበት ፡ ነው ።
በዘመናቸው ፡ ቤተ ፡ መቅደስን ፡ የሠሩ ፡ ዘሩባቤ ፲፪፤
ልና ፡ የዮሴዴቅ ፡ ልጅ ፡ ዮሴዕም ፡ ደጋግ ፡ ናቸው ፡
እናመስግናቸው ፡ ሕዝቡም ፡ ለዘለዓለም ፡ ጌት
ነት ፡ የተዘጋጀ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አከበሩት ፡
አገነኑት ።
ስም ፡ አጠራሩ ፡ ብዙ ፡ የሆነ ፡ ነሐምያንም ፡ ደግ ፡ ፲፫፤
ነው ፡ እናመስግነው ፡ የፈረሰች ፡ ቅጽርንም ፡
ሠራልኝ ፡ ደጃፍንም ፡ አቆመልኝ ፡ ቍልፍንም ፡
ሠራልን ፡ ቤታችንንም ፡ ሠራልን ።
እንደ ፡ ሄኖክ ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ የተ ፲፬፤
ፈጠረ ፡ የለም ፡ እሱንም ፡ መላእክት ፡ ከዚህ ፡
ዓለም ፡ ወደ ፡ ገነት ፡ ወሰዱት ።
እንደ ፡ ዮሴፍም ፡ ያለ ፡ ልጅ ፡ አልተወለደም ፡ ፲፭
ለወንድሞቹ ፡ አለቃ ፡ ሆነ ፡ ለወገኖቹም ፡ ምግብ ፡
ሆነ ፡ ለሰውነቶቹም ፡ ይቅርታን ፡ አገኘ ።
ሴትና ፡ ሴም ፡ ከሰው ፡ ይልቅ ፡ ከበሩ ፡ አዳምም ፡ ፲፮፤
ከነባቢት ፡ ነፍስ ፡ ከተፈጠረው ፡ ሁሉ ፡ ከበረ ።

## ምዕራፍ ፡ ፶ ።

ገናና ፡ የሆነ ፡ የካህና ፡ ልጅ ፡ ስምዖንም ፡ ፩፤
ደግ ፡ ነው ፡ እናመስግነው ፡ በዘመኑም ፡ ቤተ ፡
መቅደስን ፡ ሠራ ፡ በዘመኑም ፡ (ሄሮድስ ፡ ወልደ ፡
ሕንደፌር ፡ ቤተ ፡ መቅደስን ፡ ሠራ ፡)
ቤተ ፡ መቅደስንም ፡ ከቀድሞው ፡ አስፍቶ ፡ ፪፤
ሠራ ፡ ሊቀ ፡ ካህኑ ፡ ስምዖንም ፡ ቀጭን ፡ ልብ
ስን ፡ አሠራ ።
በዘመኑም ፡ የውሆች ፡ ምንጮች ፡ አልደረ ፫፤
ቁም ፡ የጉድጓዱም ፡ ውሀ ፡ ብዛቱ ፡ እንደ ፡ ባሕር ፡
ውሀ ፡ ሆነ ።
ወገኖቹንም ፡ ከመከራ ፡ የሚያድናቸው ፡ እሱ ፡ ፬፤
ነው ፡ ያገርም ፡ ጥሊጋ ፡ መረመረ ፡ የእስራኤል
ንም ፡ ጠላት ፡ አጠፋ ።
በእስራኤልም ፡ መመለስ ፡ ተመሰገነ ፡ የቤተ ፡ ፭፤
መቅደስንም ፡ መጋረጃ ፡ ገልጦ ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡
በደመና ፡ ግላጭ ፡ የሚወጣ ።
ከኩብ ፡ ደስ ፡ እንዲያሰኝ ፡ በምላት ፡ ቀንም ፡ ፮፤
ጨረቃ ፡ ደስ ፡ እንድታሰኝ ፡ እሱም ፡ እንደዚያ ፡
ደስ ፡ ያሰኛል ።
እግዚአብሔር ፡ በፈጠረው ፡ በጠፈር ፡ ሆና ፡ ፯፤

የምታበራ ፡ በሐይ ፡ ደስ ፡ እንድታሰኝ ፡ በቀስተ ፡
ደመናም ፡ የተሳለ ፡ ብርሃን ፡ ደስ ፡ እንዲያሰኝ ።
፰፡ በሚያገባይ ፡ ወራት ፡ የሚያብብ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡
በውሀ ፡ መፍሰሻ ፡ ያለ ፡ የሚያፈራ ፡ ተክል ፡
የደጋም ፡ መስኖ ፡ በገዘመራ ፡ ወራት ፡ ደስ ፡ እን
ዲያሰኝ ።
፱፡ በጥና ፡ እሳት ፡ ላይ ፡ ያለ ፡ ነጭ ፡ ዕጣን ፡ ተመ
ትቶ ፡ የተሠራ ፡ የወርቅ ፡ ዕቃ ።
፲፡ ፍሬዋ ፡ ብዙ ፡ የሆነ ፡ የዘይት ፡ እንጨት ፡ በጊጥ ፡
ላይ ፡ ያለ ፡ የከበረ ፡ ዕንቍ ፡ በደመና ፡ በታች ፡
ያለ ፡ ረጅም ፡ የሆነ ፡ ሰኖበር ፡ እንጨት ፡ ደስ ፡
እንዲያሰኝ ፡ እሱም ፡ እንደዚያ ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ።
፲፩፡ የሚመክበትን ፡ ልብስ ፡ በለበሰ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡
መሠዊያውም ፡ እርከን ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ በተለየ ፡
በጌትነቱም ፡ ልብስ ፡ በተመሰገነ ፡ ጊዜ ።
፲፪፡ ሥራውን ፡ በሚሠራበት ፡ በታ ፡ ቆሞ ፡ ከካህ
ናት ፡ እጅ ፡ የመሥዋዕቱን ፡ ሥጋ ፡ በተቀበለ ፡
ጊዜ ፡ ያ ፡ ደስ ፡ እንዲያሰኝ ፡ እንደዚያ ፡ ያ ፡
ደስ ፡ ያሰኝ ፡ ነበር ። ወንድሞቹ ፡ በዙሪያው ፡
ቈመው ፡ ይጋርዱት ፡ ነበር ፡ ዘምባባም ፡ ፍሬ
ውን ፡ እንደ ፡ ከብ ፡ ይከቡት ፡ ነበር ።
፲፫፡ የአሮንም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ጌጣቸውን ፡ ለብሰው ፡
ይከቡት ፡ ነበር ፡ በእስራኤል ፡ ወገኖች ፡ ሁሉ ፡
ፊት ፡ በእጃቸው ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መሥዋ
ዕት ፡ ይዘው ፡ ይቆሙ ፡ ነበር ።
፲፬፡ በመሥዋዕቱም ፡ ሥራቸውን ፡ ይሠሩ ፡ ነበር ፡
ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መሥዋ
ዕት ፡ ያዘጋጁ ፡ ነበር ።
፲፭፡ የወይኑን ፡ መሥዋዕት ፡ ይዞ ፡ እጁን ፡ አነሣ ፡ የወ
ይኑን ፡ ዘለላ ፡ ደምም ፡ አፈሰ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡
እግዚአብሔር ፡ በጎ ፡ መዓዛ ፡ አድርጎ ፡ ሊቀበ
ለው ፡ በመሠዊያው ፡ መሠረትም ፡ ያፈሰው ፡
ነበር ።
፲፮፡ የአሮንም ፡ ልጆች ፡ ምስጋናውን ፡ ይናገሩ ፡
ነበር ፡ ተመትቶ ፡ የተሠራ ፡ ነጋሪትንም ፡ ይመቱ ፡
ነበር ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ መታሰቢያ ፡
ሊሆን ፡ ቃላቸውን ፡ ያሰሙ ፡ ነበር ።
፲፯፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ አንድነት ፡ ያርፉ ፡
ነበር ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ እግር ፡ ከግምባር ፡ አድ
ርገው ፡ ይሰግዱ ፡ ነበር ፡ ሁሉን ፡ ለሚገዛ ፡ ገናና ፡
ለሆነ ፡ ለጌታቸው ፡ ለእግዚአብሔርም ፡ ይገዙ ፡
ነበር ።
፲፰፡ የሚያመሰግኑ ፡ ካህናቱም ፡ በቃላቸው ፡ ያመሰ
ግኑት ፡ ነበር ፡ የቃላቸው ፡ ዜማ ፡ ጩኸትም ፡
ቤቱን ፡ ይመላው ፡ ነበር ።
፲፱፡ ሕዝቡም ፡ ገናና ፡ ወደ ፡ ሆነ ፡ ወደ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ይለምኑ ፡ ነበር ፡ በእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡
ጸንተው ፡ ሥራቸውን ፡ እስኪጨርሱ ፡ ድረስ ፡
ይቅር ፡ በሚል ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ይለ
ምኑ ፡ ነበር ፡ ሥራቸውንም ፡ ይሠሩ ፡ ነበር ።
፳፡ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ወርዶ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ በረ
ከት ፡ ባንደበቱ ፡ ይሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ በስሙም ፡
ይመኩ ፡ ዘንድ ፡ በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ወገኖች ፡
ሁሉ ፡ ላይ ፡ እጁን ፡ አነሣ ።
እግዚአብሔር ፡ በረከቱን ፡ ያሳይ ፡ ዘንድ ፡ ዳግ ፳፩፡
መኛም ፡ ሰገዱ ።
አሁንም ፡ ሥራቱ ፡ ማዕዘን ፡ ብዙ ፡ ታምራት ፡ ፳፪፡
ያደርግ ፡ ከናታችን ፡ ማኅፀን ፡ ከተወለድን ፡
ጀምሮ ፡ ዘመናችንንም ፡ የሚያበዛ ፡ እንደ ፡ ቸር
ነቱም ፡ ይቅርታውን ፡ የሚያደርግልን ።
የልቡና ፡ ተድላ ፡ ደስታንም ፡ የሚሰጠን ፡ በዘ ፳፫፡
መናችንም ፡ ፍቅር ፡ አንድነትን ፡ የሚያደርግ ፡
ይህ ፡ ዓለም ፡ ጸንቶ ፡ በሚኖርበት ፡ ዘመን ፡ ለእ
ስራኤልም ፡ ፍቅር ፡ አንድነትን ፡ ያደረገ ።
በቸርነቱም ፡ ከእኛ ፡ ጋራ ፡ የታመነ ፡ በዘመናች ፳፬፡
ንም ፡ ከመከራው ፡ ያዳነን ፡ የሁሉን ፡ ፈጣሪ ፡
አመስግኑት ።
ሰውነቴ ፡ ሁለት ፡ ወገኖችን ፡ ጠላች ፡ ሦስተ ፳፭፡
ኛው ፡ ግን ፡ ወገኔ ፡ አይደለም ።
በፍልስጥኤምና ፡ በሰማርያ ፡ ተራራ ፡ የሚኖሩ ፡ ፳፮፡
ሰዎችን ፡ ሰውነቴ ፡ ጠላች ፡ በሰቂማ ፡ የሚኖሩ ፡
የእሞራንም ፡ ሰዎች ፡ ወገኖቼ ፡ አይደሉም ።
ከልቡናዬ ፡ ጥበብን ፡ ያነቃኋት ፡ የኢየሩሳሌሙ ፡ ፳፯፡
ሰው ፡ የአልዓዛር ፡ ልጅ ፡ የምሆን ፡ እኔ ፡ ኢያሱ ፡
ሲራክ ፡ የምክር ፡ እዝናትንና ፡ የጥበብን ፡ ትም
ርት ፡ በዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ ጻፍሁ ።
የሚያውቅ ፡ እንደዚህም ፡ ይህንን ፡ የሚያደርግ ፡ ፳፰፡
ሰው ፡ የተደነቀ ፡ ነው ፡ የሚራቀቅ ፡ ይህንንም ፡
የሚያስተውለው ፡ ሰው ፡ የተደነቀ ፡ ነው ፡ ልጄ ፡
እግዚአብሔርን ፡ ሁልጊዜ ፡ በፊትህ ፡ አድርገው ።
የእግዚአብሔር ፡ ብርሃኑ ፡ መገለጫው ፡ ነውና ፡ ፳፱፡
ይህንን ፡ ያደረገ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሁሉን ፡ ይች
ላል ።

ምዕራፍ ፡ ፶፩ ።

የሲራክ ፡ ልጅ ፡ ኢያሱ ፡ የጸለየው ፡ ጸሎት ፡ ፩፡
ይህ ፡ ነው ፡ ሰማያዊ ፡ ንጉሥ ፡ የምትሆን ፡ አቤቱ ፡
ጌታዬ ፡ እገዛልሃለሁ ፡ አቤቱ ፡ ፈጣሪዬ ፡ መድ
ኃኒቴ ፡ አመሰግንሃለሁ ።
ረዳት ፡ ሆንሃልና ፡ የምትሠውረኝም ፡ ሆንሃ ፪፡
ልና ፡ ሰውነቴንም ፡ ከሞት ፡ አድንኸዋልና ፡ የነ
ገረ ፡ ሠሪ ፡ አንደበትም ፡ ከመጣው ፡ መከራ ፡
አድንኸኛልና ፡ በስምህም ፡ አምናለሁ ። እስት
ንም ፡ ከሚሠሩዋት ፡ ከብዙ ፡ ሰዎች ፡ በጠላት
ነትም ፡ በተነሡብኝም ፡ ሰዎች ፡ ፊት ፡ የምት
ረዳኝ ፡ ሆንሃልና ፡ የምትሠውረኝ ፡ ሆንሃልና ።
እንደ ፡ ቸርነትህ ፡ ብዛት ፡ መጠን ፡ ስለ ፡ ስም ፫፡
ህም ፡ ከመከራው ፡ አዳንኸኝ ፡ እንስሳት ፡ ይበሉ ፡
ዘንድ ፡ ቀን ፡ ያዘጋጁትን ፡ ሌሊት ፡ እንዲያመ
ሰኩ ፡ እንደዚሁም ፡ ሁሉ ፡ ባገኘችኝ ፡ በመከ
ራዋ ፡ ብዛት ፡ ሰውነቴን ፡ ፈለጓት ።
ቋያ ፡ የከበበው ፡ አውሬ ፡ በእሳት ፡ መካከል ፡ ፬፡
እንዲቃጠል ።
ከሞት ፡ ሆድ ፡ ከመቃብር ፡ አደፈኛ ፡ ከሆነ ፡ ከነ ፭፡
ገረ ፡ ሠሪ ፡ አንደበትም ፡ ከሰት ፡ ነገርም ፡ አዳን
ኸኝ ።
ነገር ፡ ሠርቶ ፡ ከንጉሥ ፡ የሚያጣላ ፡ በደለኛ ፡ ፮፡
አንደበት ፡ ሰውነቴን ፡ ለሞት ፡ አደረሰው ፡ ሰው

ነቱም ፡ ለመቃብር ፡ ደረሰች ።
፯፤ በሩቱ ፡ ማዕዘን ፡ ከበቡኝ ፡ የሚረዳኝ ፡ አጣሁ ፡
የሚያድነኝ ፡ ሰው ፡ እንዳለ ፡ ብዬ ፡ አየሁ ፡ የለም ።
፰፤ አቤቱ ፡ ይቅርታህን ፡ አሰብሁ ፡ አንተን ፡ ተስፋ ፡
የሚያደርጉ ፡ ሰዎች ፡ የተደነቁ ፡ ናቸው ። ከጠ
ላቶቻቸውም ፡ ታድናቸዋለህና ፡ ዓለም ፡ ከተፈ
ጠረ ፡ ጀምሮ ፡ የነበረ ፡ ሥራህንም ፡ አሰብኩ ።
፱፤ በኃጢአቴ ፡ ከመጣብኝ ፡ መከራ ፡ አዳንኸኝ ፡
ከሞትም ፡ አድን ፡ ዘንድ ፡ ለመንኩ ።
፲፤ እግዚአብሔርን ፡ አባቴ ፡ ጌታዬ ፡ ረዳት ፡ ከሌለ ፡
ዘንድ ፡ ትዕቢተኞች ፡ በተነሡበት ፡ ወራት ፡
በመከራዬ ፡ ጊዜ ፡ አትለየኝ ፡ እለዋለሁ ።
፲፩፤ ስምህንም ፡ ለዘለዓለም ፡ አመሰግናለሁ ፡ እገዛል
ሃለሁ ፡ ምስጋናህንም ፡ እናገራለሁ ፡ ልመናዬ
ንም ፡ ሰማኸኝ ።
፲፪፤ ከሞትም ፡ አዳንኸኝ ፡ መከራ ፡ ከሚመጣበት ፡
ቀንም ፡ አዳንኸኝ ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ እገዛልሃለሁ ፡
አመሰግንሃለሁ ። አቤቱ ፡ ስምህንም ፡ አመሰግ
ናለሁ ።
፲፫፤ እኔ ፡ በሕፃንነት ፡ ሳለሁ ፡ ያለሐሰት ፡ ጥበብን ፡
መረመርኋት ፡ በጸሎቴም ፡ መረጥኋት ።
፲፬፤ በቤተ ፡ መቅደስም ፡ ስለሷ ፡ ለመንኩ ፡ ለዘለዓለ
ምም ፡ እመረምራታለሁ ።
፲፭፤ ምሥጢሯም ፡ እንደ ፡ ተክል ፡ ፍሬ ፡ በዛልኝ ፡
ልቡናዬንም ፡ በሷ ፡ ደስ ፡ አሰኘ ፡ እግሬ ፡ ልቡና
ዬም ፡ በውነት ፡ ጸናች ፡ ከሕፃንነቴም ፡ ጀምሬ ፡
ምሥጢሯን ፡ መረመርኩ ።
፲፮፤ በጆሮዬም ፡ ፈጽሚ ፡ አደመጥኩ ፡ መረጥኋት ፡
እኔም ፡ ብዙ ፡ ጥበብን ፡ አገኘሁ ።
፲፯፤ በሷም ፡ ከፍታ ፡ ተደረገልኝ ፡ ጥበብን ፡ የገለጠ
ልኝ ፡ እግዚአብሔርንም ፡ አመሰግነዋለሁ ።
፲፰፤ አደርጋትም ፡ ዘንድ ፡ አሰብሁ ፡ ለበጎ ፡ ነገርም ፡
ቀናሁ ፡ መከራም ፡ መጥቶብኝ ፡ አላፍርም ።
፲፱፤ ሰውነቴም ፡ በሷ ፡ ተበረታታች ፡ በሥራዬም ፡
ተራቀቅሁ ፡ እጆቼንም ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ አንሣ
ሁ ፡ አድንቆርናዬም ፡ አለቀስሁላት ።
ሰውነቴንም ፡ ከሷ ፡ አቀናሁ ፡ በሚገባ ፡ በሱ ፡ ፳፤
ፈቃድ ፡ አገኘኋት ፡ ልቡናዬንም ፡ ከሷ ፡ ጋራ ፡
አጸናሁ ፡ ስለዚህም ፡ ነገር ፡ እግዚአብሔር ፡ በመ
ከራው ፡ አልጣለኝም ።
ሰውነቴም ፡ በሷ ፡ ታወከ ፡ መረመረቻት ፡ ስለ ፳፩፤
ዚህ ፡ ነገር ፡ ያማረ ፡ ትምህርትን ፡ ገንዘብ ፡ አደ
ረግሁ ።
እግዚአብሔርም ፡ የጸሎቴን ፡ ዋጋ ፡ ሰጠኝ ፡ ፳፪፤
በሷም ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰግነዋለሁ ።
እናንተ ፡ ሰነፎች ፡ ወደኔ ፡ ቅረቡ ፡ በጥበብ ፡ ቤት ፡ ፳፫፤
ትኖራላችሁ ።
እንደምን ፡ አጣችኋት ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ንገሩ ፳፬፤
ልኝ ፡ ሰውነታችሁስ ፡ ከትምህርት ፡ ፈጽማ ፡
እንደምን ፡ ተጠማች ።
እንደበቴንም ፡ ገልጬ ፡ ተናገርኩ ፡ ያለዋጋም ፡ ፳፭፤
አስተማርኋችሁ ።
ክሣደ ፡ ልቡናችሁንም ፡ አዋርዳችሁ ፡ ምሥጢ ፳፮፤
ሯንም ፡ መርምሩ ፡ ሰውነታችሁም ፡ ጥበብን ፡
ትቀበል ፡ ጥበብንም ፡ ማግኘት ፡ ቅርብ ፡ ነው ።
ጥቂት ፡ ድካምን ፡ ደክሜ ፡ በሷ ፡ ብዙ ፡ ዕረፍ ፳፯፤
ትን ፡ እንዳገኘሁ ፡ እነሆ ፡ በዓይናችሁ ፡ እስተ
ውሉ ።
ኩብዙ ፡ ገንዘብ ፡ ቍጥር ፡ ከሌለው ፡ ከወርቅ ፡ ፳፰፤
ይልቅ ፡ ጥበብን ፡ መረጥኋት ፡ ለናንተም ፡ አስ
ተማርኋችሁ ።
ሰውነቴንም ፡ በቸርነቱ ፡ ደስ ፡ አላት ፡ እግዚአ ፳፱፤
ብሔርንም ፡ ማመስገን ፡ ቸል ፡ አትበሉ ።
በጊዜው ፡ ጊዜ ፡ ዋጋችሁን ፡ ይሰጣችሁ ፡ ዘንድ ፡ ፴፤
ይህ ፡ ዓለም ፡ የሚያልፍበት ፡ ጊዜው ፡ ሳይደ
ርስ ፡ ሥራችሁን ፡ ሥሩ ።

ለእግዚአብሔር ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ክብር ፡ ምስ
ጋና ፡ ይግባውና ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ሰው ፡ የአል
ዓዛር ፡ ልጅ ፡ ሲራክ ፡ ኢያሱ ፡ የተናገረው ፡
ጥበብ ፡ መላ ፡ ተፈጸመ ።

# የምናሴ ጸሎት

የንጉሡ ፡ የሕዝቅያስ ፡ ልጅ ፡ ምናሴም ፡ ጸለየ ፡
እንዲህም ፡ አለ ፦
፩ ዓለምን ፡ ሁሉ ፡ የምትገዛ ፥
የአባቶቻችን ፡ የአብርሃምና ፡ የይስሐቅ ፡
የያዕቆብም ፡ የጻድቃን ፡ ልጆቻቸውም ፡
አምላክ ፡ ሆይ ፥
ሰማይንና ፡ ምድርን ፡ ከዓለሞቻቸው ፡ ጋር ፡
የፈጠርህ ፥
፪ በቃልህ ፡ ትእዛዝ ፡ ባሕርን ፡ የገሠጽሃት ፥
ቀላዮችን ፡ የዘጋህ ፥ የሚያስፈሩውንም ፡
የወሰንህ ፥
፫ ይኸውም ፡ በተመሰገነ ፡ ስምህ ፡ ነው ፥
ኃይልህ ፡ ከመገለጡ ፡ የተነሣ ፡ ሁሉ ፡ የሚ
ርድ ፡ የሚንቀጠቀጥ ፤
፬ ለክብርህ ፡ ከፍተኛነት ፡ ፍጻሜ ፡ የለውምና ፥
የቍጣህ ፡ መቅሠፍት ፡ በኃጥአን ፡ ላይ ፡
ግሩም ፡ ነው ።
፭ በትእዛዝህ ፡ ለሚሆነው ፡ ይቅርታ ፡ ስፍር ፡
ቍጥር ፡ የለውም ፤
ገናና ፡ እግዚአብሔር ፡ አንተ ፡ ብቻ ፡ ነህና ፥
ይቅር ፡ ባይ ፥ ከቍጣ ፡ የራቅህ ፥ ይቅርታህ ፡
የበዛ ፥
የሰውንም ፡ ኃጢአት ፡ የምታስተሰርይ ፡
አንተ ፡ ነህ ።
፮ አሁንም ፥ አቤቱ ፥ የጻድቃን ፡ አምላካቸው ፡
አንተ ፡ ነህ ።
ንስሓን ፡ የፈጠርህ ፡ ለጻድቅ ፡ ሰው ፡ አይደ
ለምና ፥
አንተን ፡ ላልበደሉ ፡ ለአብርሃምና ፡ ለይስ
ሐቅ ፡ ለያዕቆብም ፡ አይደለምና ፥
የእኔን ፡ የኃጥኡን ፡ ንስሓ ፡ ወደ ፡ ማየት ፡
ተመለስ ፡ እንጂ ።
፯ ቍጥሩ ፡ ከባሕር ፡ አሸዋ ፡ የሚበልጥ ፡ በደ
ልን ፡ በድያለሁና ፡ ኃጢአቴም ፡ ብዙ ፡
ነውና ፤
ከበደሌም ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ ቀና ፡ ብዬ ፡ የሰ
ማይን ፡ ርዝመት ፡ አይ ፡ ዘንድ ፡ አገባቤ ፡
አይደለም ።
ሰውነቴን ፡ ከኃጢአቴ ፡ አሳርፋት ፡ ዘንድ ፡ በብ
ረት ፡ ቀፎ ፡ ያከምሁ ፥

በዚህም ፡ ደግሞ ፡ አላረፍሁም ፤
መዓትህን ፡ አነሣሥቻለሁና ፥ ፰
ከንቱውን ፡ ስመለከት ፡ የማይጠቅመኝንም ፡
ነገር ፡ ሳበዛ ፡ በፊትህ ፡ ክፉ ፡ ሥራን ፡ ሠር
ቻለሁና ።
አሁንም ፡ ቸርነትህን ፡ እየለመንሁ ፡ በልቤ ፡ ፱
ጉልበት ፡ እሰግዳለሁ ።
አቤቱ ፡ ጌታዬ ፥ ፈጽሚ ፡ በደልሁ ፥ ፲
ኃጢአቴንም ፡ አምን ፡ እላለሁ ።
አንተን ፡ እማልዳለሁ ፡ እለምንሀማለሁ ፤ ፲፩
ይቅር ፡ በለኝ ፥ አቤቱ ፥ ይቅር ፡ በለኝ ፤
ለኃጢአቴም ፡ አሳልፈህ ፡ አትስጠኝ ።
ለዘላለም ፡ ክፋቴን ፡ አትመልከትብኝ ፤ ፲፪
በምድር ፡ ጥልቀት ፡ አትበቀለኝ ፤
በንስሓ ፡ ለሚመለሱ ፡ ሰዎች ፥ አቤቱ ፥
አምላካቸው ፡ አንተ ፡ ነህና ፡
ቸርነትህ ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ይገለጥ ፤ መዳን ፡ የማ
ይገባኝ ፡ ሲሆን ፡ በይቅርታህ ፡ ብዛት ፡
አዳንኸኝ ።
በየጊዜውና ፡ በሕይወቴ ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ አመ ፲፫
ሰግንሃለሁ ።
የሰማያት ፡ ኃይል ፡ ሁሉ ፡ አንተን ፡ ያመሰግ
ናሉና ፤
ለዘላለምም ፡ ምስጋና ፡ ለአንተ ፡ ይገባል ፤
አሜን ።

# ተረፈ ኤርምያስ

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

እግዚአብሔር ፡ ያዘዘውን ፡ ይነግራቸው ፡
ዘንድ ፡ የባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ ማርኮ ፡ ወደ ፡ ባቢ
ሎን ፡ አገር ፡ ወደ ፡ ወሰዳቸው ፡ ሰዎች ፡ ኤርም
ያስ ፡ የላካቸው ፡ የጣዖቱን ፡ መልክ ፡ የሚናገር ፡
መጣፍ ፡ ይህ ፡ ነው ።
፪፤ እስከ ፡ ሰባተኛ ፡ ትውልድ ፡ ድረስ ፡ በዚያ ፡ በባ
ቢሎን ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ ትኖሩ ፡ ዘንድ እግዚአ
ብሔርን ፡ ስለ ፡ በደላችሁበት ፡ ኃጢአታችሁ ፡
ማርከው ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ወሰዷችሁ ።
፫፤ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ከዚያ ፡ ቦታ ፡ በትድላ ፡ በደ
ስታ ፡ አወጣችኋለሁ ፡ አለ ።
፬፤ አሁን ፡ ግን ፡ የብርና ፡ የወርቅ ፡ የንጨት ፡ የሆኑ ፡
የባቢሎን ፡ ጣዖቶችን ፡ ታያላችሁ ፡ በጫንቃ
ቸው ፡ ይሸከሟቸዋል ፡ አሕዛብንም ፡ ያስፈሯ
ቸዋል ።
፭፤ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ እንደነሱ ፡ እንዳትሆኑ ፡ እወቁ ።
፮፤ አሕዛብን ፡ በኋላቸውና ፡ በፊታቸው ፡ ሁነው ፡
ሲሰግዱላቸው ፡ ብታዩ ፡ በልቡናችሁ ፡ አቤቱ ፡
ስግደትስ ፡ ላንተ ፡ ይገባል ፡ በሉ ።
፯፤ እንደበትም ፡ ቢኖራቸው ፡ ጃን ፡ ሸላሚ ፡ የሠ
ራው ፡ ነው ፡ ይኸውም ፡ የብርና ፡ የወርቅ ፡ ነው ፡
እነርሱ ፡ አሰተኞች ፡ ናቸው ፡ መናገርም ፡ አይ
ችሉም ።
፰፤ ቆንጆ ፡ ልጅ ፡ በወርቅ ፡ ጌጥ ፡ እንድታጌጥ ።
፱፤ እነሱም ፡ የብርና ፡ የወርቅ ፡ ቀጸላ ፡ ሠሩላቸው ።
፲፤ እንደ ፡ ሰውም ፡ ያለብሷቸዋል ።
፲፩፤ ዝግታቸውንም ፡ ከራሳቸው ፡ አያርቁም ።
፲፪፤ በነጭ ፡ ሐር ፡ ይሸፍኗቸዋል ፡ ከቤትም ፡ ትቢያ ፡
የተነማ ፡ ያኘቸዋል ።
፲፫፤ እንደ ፡ ሰውም ፡ በትር ፡ ያሲዟቸዋል ፡ ነገር ፡
ግን ፡ የበደላቸውን ፡ ሰው ፡ አይበቀሉትም ።
፲፬፤ ገጀሞም ፡ በጁ ፡ የተያዘ ፡ አለ ፡ ራሱን ፡ ግን ፡
ከሌቦች ፡ አያድንም ፡ አማልክት ፡ እንዳይደሉ ፡
በዚህ ፡ ይታወቃሉ ፡ እናንተም ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡
አትፍሩዋቸው ።
፲፭፤ የዘይት ፡ ሸክላዎች ፡ እንዲሰበሩ ፡ እንዳይረቡ ፡
እንዳይጠቅሙም ፡ አማልክቶቻቸውም ፡ እንደ
ዚህ ፡ አይረቡም ፡ አይጠቅሙም ።
፲፮፤ በቤትም ፡ ይቸነክሯቸዋል ፡ ከሚወጣው ፡ ከሚ
ገባውም ፡ ሰው ፡ ሥራ ፡ የተነማ ፡ ትቢያው ፡
በይናቸው ፡ ይገባል ።
፲፯፤ ሌቦች ፡ እንዳይሠርቋቸው ፡ ከሀናቶቻቸው ፡
ይዘጉባቸዋል ።
፲፰፤ መብራት ፡ ያበሩላቸዋል ፡ የሚያዩት ፡ ነገር ፡
የለም ፡ ልብሶቻቸውንም ፡ ቢቀሟቸው ፡ አያ
ውቁም ።
፲፱፤ በቤትም ፡ ከሚያጤሱት ጢስ ፡ የተነማ ፡ ፊታ
ቸው ፡ ይጠቊራል ፡ በራሶቻቸውም ፡ የሌት ፡
ወፍ ፡ ሌሎችም ፡ ወፎች ፡ ድመቶችም ፡ ይቀ
መጡባቸዋል ፤
፳፤ በዚህ ፡ አማልክት ፡ እንዳይደሉ ፡ ታውቃላ
ችሁ ፡ እንግዲህም ፡ ወዲያ ፡ አትፍሩዋቸው ።
፳፩፤ ወርቅን ፡ ቀብረው ፡ ቢያኖሩት ፡ ካልወለወሉት ፡
እንዳያበራ ፡ እነሱንም ፡ መትተው ፡ ቢሠሩዋ
ቸው ፡ አያውቁም ።
፳፪፤ እስትንፋስ ፡ የሌላቸው ፡ ጉስቊልናቸውም ፡
ይታወቅ ፡ ዘንድ ፡ በጫንቃቸው ፡ ይሸከሟቸ
ዋል ።
፳፫፤ ወደ ፡ መሬትም ፡ ቢወድቁ ፡ እነሱ ፡ አውቀው ፡
አይነሡም ።
፳፬፤ ሰዎቹም ፡ ቢያነሥዋቸው ፡ እነሱ ፡ አይቆሙም ፡
እንደ ፡ ሞተ ፡ ሰው ፡ መብልን ፡ መሥዋዕትንም ፡
ያቀርቡላቸዋል ።
፳፭፤ ካህናቶቹ ፡ ይበሉታል ፡ እንጂ ፡ እነሱ ፡ አይበሉ
ትም ፡ አማልክት ፡ እንዳይደሉም ፡ በዚህ ፡ እወቁ ፡
አትፍሯቸው ። እነሱ ፡ ደንጊያና ፡ እንጨት ፡
ናቸው ።
፳፮፤ ቢረግሙላቸውም ፡ አይሰሙም ፡ ክፉና ፡ በጎ ፡
ሥራ ፡ መሥራትም ፡ አይችሉም ፡ አያነግሡም ፡
አይሽሩም ፡ አያከብሩም ፡ አያደኸዩም ፡ አይገ
ድሉም ፡ አያድኑም ። ደካማውን ፡ ከሚቀማው ፡
ሰው ፡ እጅ ፡ አያድኑትም ።

ወራሪም ፡ ቢመጣባቸው ፡ ከሀናቶቻቸው ፡ ምስ ፳፯፤
ላቸውን ፡ የሚሠውሩበት ፡ ቦታ ፡ ይፈልጋሉ ።
ራሳቸውን ፡ የማያድኑ ፡ እስዚህ ፡ እንዴት ፡ አም ፳፰፤
ላኮች ፡ ይሆናሉ ፡ እነሱም ፡ የሰው ፡ እጅ ፡ ሥራ ፡
እንደ ፡ ሆኑ ፡ ይታወቃሉ ፡ ያምላክነትም ፡ ሥራ ፡
የላቸው ።
አያዘንሙም ፡ ቢዘንቡም ፡ አይከለክሉም ፡ ቊራ ፳፱፤
ዎች ፡ በምድርና ፡ በሰማይ ፡ መካከል ፡ እንዲ
ኖሩ ፡ እነሱ ፡ በመካከል ፡ ይኖራሉ ።
የጣዖታቱም ፡ ቤት ፡ ቢቃጠል ፡ ካህናቱ ፡ ሸሽ ፴፤
ተው ፡ ራሳቸውን ፡ ያድናሉ ፡ እነሱ ፡ ግን ፡
እንደ ፡ ምሰሶ ፡ በመካከል ፡ ቆመው ፡ ይቃጠ
ላሉ ።
ጠላታቸውን ፡ የማይበቀሉ ፡ ራሳቸውንም ፡ ፴፩፤
ከሌባ ፡ የማያድኑ ፡ እነዚህ ፡ እንዴት ፡ አማል
ክት ፡ ናቸው ።
ሐሰተኞች ፡ ናቸው ፡ አምላኮች ፡ አይደሉም ፡ ፴፪፤
ከነሱስ ፡ መግጊያ ፡ ይሻላል ። በቤት ፡ ውስጥ ፡
ያለውን ፡ ያድናል ። አይራገሙም ፡ አይመረ
ቁም ፡ በሰማይም ፡ ምልክት ፡ አያሳዩም ፡ እንደ ፡
ጨረቃና ፡ እንደ ፡ ፀሐይም ፡ አያበሩም ።
ከነሱስ ፡ ሸሽቶ ፡ የሚድን ፡ ከብት ፡ ይሻላቸዋል ፡ ፴፫፤
( ይበልጣል ፡ ) ፊሳ ፡ በጨለማ ፡ እንዲኖር ፡ ጣዖ
ቶቻቸውም ፡ እንደዚያ ፡ ናቸው ፡ ከዚህም ፡
ሁሉ ፡ ጣዖት ፡ የሌለው ፡ ከስድብም ፡ የራቀ ፡
ሰው ፡ ይሻላል ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

ኤርምያስ ፡ የተናገረው ፡ ትንቢት ፡ ይህ ፡ ነው ።
ኤርምያስ ፡ ጳስኮርን ፡ እናንተስ ፡ ባለ ፡ ዘመና ፪፤
ችሁ ፡ ሁሉ ፡ ሃይማኖትን ፡ እንዳባቶቻችሁ ፡
ትጣሷታላችሁ ፡ ከናንተም ፡ በኋላ ፡ የሚመጡ ፡
ልጆቻችሁም ፡ አይጠብቋትም ።
እነሱስ ፡ ካባቶቻችሁ ፡ ይልቅ ፡ ፈጽማ ፡ የተና ፫፤
ቀች ፡ ኃጢአትን ፡ ሠሩ ። እነሱ ፡ ዋጋ ፡ የሌ
ለው ፡ ክርስቶስን ፡ ይሸጡታል ፡ ከበሽታ ፡ የሚ
ያድን ፡ ጌታን ፡ እንዲታመም ፡ ያደርጉታል ፡
ኃጢአት ፡ የሚያስተሠርይ ፡ ጌታንም ፡ ይፈር
ዱበታል ።
እስራኤል ፡ ልጆች ፡ የተስማሙበት ፡ የክርስ ፬፤
ቶስን ፡ ዋጋ ፡ ሠላሳውን ፡ ብር ፡ ይቀበሉታል ፡
ያንንም ፡ ብር ፡ ለሸክላ ፡ ሠሪ ፡ ቦታ ፡ ዋጋ ፡ አድ
ርገው ፡ ይሰጡታል ።
እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘኝ ፡ እናገራለሁ ። ፭፤
ፈርደው ፡ ንጹሕ ፡ ደምን ፡ አፍሰዋልና ፡ ይህን ፡ ፮፤
ስላደረጉ ፡ ጥፋቱና ፡ መከራው ፡ አስቀድሞ ፡
በነሱ ፡ ከነሱም ፡ በኋላ ፡ በልጆቻቸው ፡ ይወር
ድባቸዋል ።
የባቢሎን ፡ ሰዎች ፡ በማረኳቸው ፡ ጊዜ ፡ ተሠ ፯፤
ውሮ ፡ የማይቀር ፡ ባሮክ ፡ የተናገረው ፡ ብዙ ፡
ነገር ፡ ይህ ፡ ነው ።
የከለዳውያን ፡ ንጉሥ ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ፰፤
በማረካቸው ፡ ጊዜ ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ኤርምያስን ፡ ተናገረው ።
ወዳጄ ፡ ኤርምያስ ፡ ከዚች ፡ አገር ፡ ውጣ ፡ ከሚ ፱፤
ኖሩባት ፡ ሰዎች ፡ ኃጢአት ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡
አገሪቱን ፡ አጠፋታለሁና ፡ አንተ ፡ ውጣ ፡ ባሮ
ክም ፡ ይውጣ ፡ አለው ።
እስካሁን ፡ አለማጥፋቴ ፡ ልመናህ ፡ በመካከሷ ፡ ፲፤
እንደ ፡ ጽኑ ፡ ምሰሶ ፡ በዙሪያዋም ፡ እንደ ፡ አድ
ማስ ፡ ቅጥር ፡ ሆኗልና ፡ ስለዚህ ፡ ነው ፡ የከለዳ
ውያን ፡ ሠራዊት ፡ ሳይመጣ ፡ አገሪቱንም ፡ ሳይ
ከብት ፡ አሁንም ፡ ተነሥታችሁ ፡ ሒዱ ፡ ውጡ ።
ኤርምያስም ፡ ጌታዬ ፡ እለምንሃለሁ ፡ እኔን ፡ ፲፩፤
ባሪያህን ፡ በፊትህ ፡ እናገር ፡ ዘንድ ፡ እዘዘኝ ፡
ብሎ ፡ ተናገረ ።
እግዚአብሔርም ፡ ወዳጄ ፡ ኤርምያስ ፡ በል ፡ ፲፪፤

ተናገር ፡ አለው ።
፲፪፤ ኤርምያስም ፡ ተናገረ ፡ ሁሉን ፡ የምትገዛ ፡ አቤቱ ፡
ንጉሡ ፡ ከሠራዊቱ ፡ ጋራ ፡ ይታይ ፡ ዘንድ ፡
በሬማሬ ፡ አገር ፡ በኢየሩሳሌምም ፡ በረታሁ
በት ፡ ይል ፡ ዘንድ ፡ የመረጥከት ፡ ይቺን ፡ አገር ፡
በከለዳውያን ፡ እጅ ፡ ታጠፋታለህን ፡ አለው ።
፲፫፤ አቤቱ ፡ አይገባህም ፡ መጥፋቷንም ፡ ከወደድህ ፡
በሥልጣንህ ፡ አጥፋት ፡ አለው ።
፲፬፤ እግዚአብሔርም ፡ ኤርምያስን ፡ በሚኖሩባት ፡
ሰዎች ፡ ኃጢአት ፡ አጠፋታለሁና ፡ አንተ ፡
ወዳጄ ፡ ስለሆንክ ፡ ባሮክና ፡ አንተ ፡ ተነሥታ
ችሁ ፡ ውጡ ።
፲፭፤ እኔ ፡ አስቀድሜ ፡ በሮቿን ፡ ካልከፈትሁ ፡ ንጉሡ ፡
ሠራዊቱም ፡ ወዳገሪቱ ፡ መግባት ፡ አይቻለ
ውም ።
፲፮፤ አሁንም ፡ ተነሥተህ ፡ ወደ ፡ ባሮክ ፡ ሒድ ፡ ይህን
ንም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ንገረው ፡ የሌሊቱ ፡ ስድስት ፡
ሰዓት ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ ተነሥታችሁ ፡ ወዳገሪቱ ፡
ቅጥር ፡ ኑ ።
፲፯፤ እኔም ፡ አሳያችኋለሁ ፡ እኔም ፡ አስቀድሜ ፡ አገ
ሪቱን ፡ ካላጠፋኋት ፡ ወደሷ ፡ መግባት ፡ አይች
ሉም ።
፲፰፤ እግዚአብሔርም ፡ ይህንን ፡ ተናግሮ ፡ ከኤርም
ያስ ፡ ዘንድ ፡ ሔደ ።
፲፱፤ ያንጊዜ ፡ ልብሱን ፡ ቀደደ ፡ በራሱም ፡ ትቢያ ፡
ነሰነሰ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ መቅደስም ፡ ገባ ።
፳፤ ባሮክም ፡ ኤርምያስን ፡ በራሱ ፡ ትቢያ ፡ ነስንሶ ፡
ልብሶቹን ፡ ቀዶ ፡ ባየው ፡ ጊዜ ፡ አባቴ ፡ ኤርም
ያስ ፡ ምን ፡ ሆንክ ፡ ሕዝቡስ ፡ ምን ፡ ኃጢአት ፡
ሠሩ ፡ ብሎ ፡ ቃሉን ፡ አሰምቶ ፡ ጮኸ ።
፳፩፤ ሕዝቡ ፡ በሳቱ ፡ ጊዜ ፡ ኤርምያስ ፡ ያዝን ፡ ነበ
ርና ፡ በራሱም ፡ አመድ ፡ ትቢያ ፡ ይነሰንስ ፡ ነበ
ርና ፡ የሕዝቡም ፡ በደላቸው ፡ እስኪሠረይላ
ቸው ፡ ድረስ ፡ ለሕዝቡም ፡ ይጸልይላቸው ፡ ነበ
ርና ።
፳፪፤ ባሮክ ፡ አባቴ ፡ ኤርምያስ ፡ ምን ፡ ሆንክ ፡ ብሎ ፡
ጠየቀው ። ኤርምያስም ፡ ልቡናችንን ፡ ከደ
ስታ ፡ እንለየው ፡ እንጂ ፡ ልብሶቻችንን ፡ እንዳ
ንቀድ ፡ ጠብቅ ፡ (እወቅ ፡) አለው ።
፳፫፤ ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ እነዚህን ፡ ወገኖች ፡ ይቅር ፡
አይሏቸውምና ፡ እንባን ፡ እስክንመላቸው ፡
ድረስ ፡ በሚገባ ፡ እናለቅስ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ጕድ
ጓዶች ፡ ውኃን ፡ እንጨምር ፡ አለው ።
፳፬፤ ባሮክም ፡ አባቴ ፡ ኤርምያስ ፡ ምን ፡ ሆንክ ፡ አለ ።
፳፭፤ ኤርምያስም ፡ ይቺን ፡ አገር ፡ በከላውዴዎን ፡
ንጉሥ ፡ እጅ ፡ ያጠፋታልና ፡ አሕዛብም ፡ ሕዝ
ቡን ፡ በክፉ ፡ ነገር ፡ ይማርኳቸዋልና ፡ ስለዚህ ፡
ነው ፡ አለው ።
፳፮፤ ባሮክም ፡ ይህንን ፡ ሁሉ ፡ ነገር ፡ ሰምቶ ፡ አባቴ ፡
ኤርምያስ ፡ ምን ፡ ሰማህ ፡ አለ ፡ እሱም ፡ ልብሶ
ቹን ፡ ቀደደ ፡ ነገሥታቱ ፡ ምን ፡ ላኩብህ ፡ አለው ።
፳፯፤ ኤርምያስም ፡ ነገሩን ፡ በውነት ፡ ታውቅ ፡ ዘንድ ፡
ከሌሊቱ ፡ እስከ ፡ ስድስት ፡ ሰዓት ፡ ድረስ ፡ ከኔ ፡
ጋር ፡ ቆይ ፡ አለው ።
እያለቀሱ ፡ በቤተ ፡ መቅደስም ፡ ተቀመጡ ፡ ፳፰፤
ከሌሊቱም ፡ ስድስት ፡ ሰዓት ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡ እግ
ዚአብሔር ፡ ኤርምያስን ፡ ይወጣ ፡ ዘንድ ፡ ውጣ ፡
አለው ።
ከባሮክ ፡ ጋር ፡ ወጣ ፡ ወደ ፡ ቅጽሩም ፡ ደረሱ ፡ ፳፱፤
እየጸለዩ ፡ በቅጽሩ ፡ ተቀመጡ ።
ውጋ ፡ ውጋ ፡ የሚል ፡ ነጋሪት ፡ ተሰማ ፡ መላእክ ፴፤
ትም ፡ ከሰማይ ፡ መጡ ፡ በጃቸውም ፡ መብራት ፡
ይዘው ፡ በቅጥሯ ፡ ቆመው ፡ ነበር ።

ምዕራፍ ፡ ፰ ።

ያንጊዜ ፡ ኤርምያስና ፡ ባሮክ ፡ የዚህ ፡ ነገር ፡ ፩፤
ምልክት ፡ በውነት ፡ እንደ ፡ ተገኘ ፡ ዛሬ ፡ አወ
ቅን ፡ ብለው ፡ አለቀሱ ።
ኤርምያስም ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንዲት ፡ ነገርን ፡ ፪፤
እስክለምነው ፡ ድረስ ፡ አገሩን ፡ ሁሉ ፡ እንዳታ
ጠፉ ፡ እለምናችኋለሁ ፡ ብሎ ፡ መላእክትን ፡
ለመናቸው ።
ጌታም ፡ ከወዳጄ ፡ ከኤርምያስ ፡ ጋራ ፡ እስክነጋ ፫፤
ገር ፡ ድረስ ፡ አገሪቱን ፡ አታጥፉ ፡ ብሎ ፡ ለመላ
እክት ፡ ነገራቸው ።
ኤርምያስም ፡ ያንጊዜ ፡ ጌታዬ ፡ እለምንሃለሁ ፡ ፬፤
ካንተ ፡ ጋር ፡ እናገር ፡ ዘንድ ፡ እዘዘኝ ፡ ብሎ ፡
ተናገረ ፡ ጌታም ፡ ወዳጄ ፡ ኤርምያስ ፡ የምትወ
ደውን ፡ ነገር ፡ ተናገር ፡ አለው ።
ኤርምያስም ፡ አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ ይቺን ፡ አገር ፡ ፭፤
በጠላቷ ፡ እጅ ፡ አሳልፈህ ፡ እንድትሰጣት ፡ የባ
ቢሎንም ፡ ወገኖች ፡ እንዲይዟት ፡ እነሆ ፡ ዛሬ ፡
አወቅሁ ፡ አለው ።
ተሠውረን ፡ ስለምናገለግልባት ፡ ንዋየ ፡ ቅድ ፮፤
ሳት ፡ ምን ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ ትወዳለህ ፡ በላያ
ቸውስ ፡ ምን ፡ አደርግ ፡ ዘንድ ፡ ትወዳለህ ፡
አለው ።
ጌታም ፡ እነሱን ፡ ወስደህ ፡ በምድር ፡ በቤተ ፡ ፯፤
መቅደስ ፡ አደራ ፡ ስጣት ፡ አንቺ ፡ ምድር ፡ በው
ኆች ፡ ላይ ፡ የፈጠረሽ ፡ በሰገነት ፡ ክፍልም ፡
የከፈለሽ ፡ የፈጣሪሽ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡
ሰምተሽ ፡ ጌጥሽን ፡ ተቀበዪ ፡ ዘሩባቤል ፡ እስኪ
መጣ ፡ ድረስ ፡ ገንዘብሽንም ፡ ጠብቂ ፡ በላት ፡
አለው ።
ኤርምያስም ፡ ጌታዬ ፡ እለምንሃለሁ ፡ ሕዝቡን ፡ ፰፤
ብዙ ፡ ዘመን ፡ ለጠበቃቸው ፡ ባሪያህ ፡ ኤርምያ
ስንም ፡ ካገሩ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ይልቅ ፡ ለጠበቀኝ ፡
ለኢትዮጵያው ፡ ሰው ፡ ለአቤሜሌክ ፡ የማደር
ገውን ፡ ግለጥልኝ ፡ ብሎ ፡ ተናገረ ።
እርሱ ፡ ከረግረግ ፡ ጕድጓድ ፡ አወጣኝ ፡ እንዳያ ፱፤
ዝን ፡ ያገሪቱን ፡ ጥፋት ፡ ያይ ፡ ዘንድ ፡ አልወድ
ለትም ፡ አለ ።
ጌታም ፡ ለኤርምያስ ፡ ወደ ፡ አግሪጳስ ፡ ወይን ፡ ፲፤
በታ ፡ በዚህ ፡ ተራራ ፡ ጐዳና ፡ አቤሜሌክን ፡
ላከው ፡ ሕዝቡን ፡ ወዳገራቸው ፡ እስክመልሳ
ቸው ፡ ድረስ ፡ እኔ ፡ እሠውረዋለሁ ።
ኤርምያስ ፡ አንተም ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ አገር ፡ ፲፩፤
እስክትደርስ ፡ ድረስ ፡ ከሕዝቡ ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡

ግብፅ ፡ ሂድ ፡ ወዳገራቸው ፡ እስክመልሳቸው ፡
ድረስ ፡ ስታስተምራቸው ፡ ኑር ።
፲፪ ባሮክን ፡ ግን ፡ በዚያ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ተወው ፡
ጌታም ፡ ይህንን ፡ ሁሉ ፡ ነገር ፡ ለኤርምያስ ፡ ነግ
ሮት ፡ ከኤርምያስ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ አልፎ ፡
ሄደ ።
፲፫ ባሮክና ፡ ኤርምያስም ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡
ገቡ ፡ የሚያገለግሉበትንም ፡ ሰቃ ፡ ሁሉ ፡ ጌታ ፡
እንዳዘዛቸው ፡ ለምድር ፡ ሰጡት ፡ ምድርም ፡
ያንጊዜ ፡ ተቀብላ ፡ዋጠችው ።
፲፬ ሁሉቱም ፡ ሁሉ ፡ ተቀምጠው ፡ አለቀሱ ፡ በማ
ግሥቱ ፡ በነጋ ፡ ጊዜ ፡ ኤርምያስ ፡ አቤሜሌክን ፡
ተራንተራውን ፡ ያዘህ ፡ ወደ ፡ አግሪጳስ ፡ ወይን ፡
ቦታ ፡ በተራራው ፡ ጎዳና ፡ ሂድ ፡ የእግዚአብ
ሔር ፡ ረድኤት ፡ ጌትነቱም ፡ ባንተ ፡ ራስ ፡ አድ
ሯልና ፡ ለታመመው ፡ ወገኖች ፡ ትንሽ ፡ በለስን ፡
አምጣ ፡ ብሎ ፡ ላከው ።
፲፭ እሱም ፡ እንዳዘዘው ፡ ሔደ ፡ በማግሥቱ ፡
በነጋ ፡ ጊዜ ፡ የከለዳውያን ፡ ሠራዊት ፡ አገሪቱን ፡
ከበቧት ፡ ታላቁም ፡ መልአክ ፡ ነጋሪቱን ፡ መታ ።
፲፮ እሱም ፡ የከለዳውያን ፡ ሠራዊት ፡ ግቡ ፡ እነሆ ፡
በሮቹም ፡ ይከፈቱላችኋል ፡ አለ ።
፲፯ ያንጊዜም ፡ ንጉሡ ፡ ከሠራዊቱ ፡ ጋር ፡ ገብቶ ፡
ሕዝቡን ፡ ሁሉ ፡ ማረከ ።
፲፰ ያንጊዜም ፡ ኤርምያስ ፡ የቤተ ፡ መቅደሱን ፡
መክፈቻ ፡ ይዞ ፡ ከከተማ ፡ ወደ ፡ ውጪ ፡ ወጣ ።
፲፱ ይህንንም ፡ መክፈቻ ፡ ፀሐይ ፡ የእግዚአብሔር ፡
ማደሪያ ፡ የቤተ ፡ መቅደስን ፡ መክፈቻ ፡ ተቀ
በል ፡ ብሎ ፡ በፀሐይ ፡ ፊት ፡ ጣለው ።
፳ ኃጢአታችንን ፡ እኛ ፡ እየተከባከብናት ፡ ስለተ
ገኘን ፡ ከተወለድን ፡ ጀምሮ ፡ እሱን ፡ ለመጠ
በቅ ፡ አይገባንምና ፡ እግዚአብሔር ፡ የሱን ፡
ነገር ፡ እስከሚነግርህ ፡ እስከ ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡
ድረስ ፡ ጠብቀው ፡ አለው ።
፳፩ ኤርምያስም ፡ ለወገኖቹ ፡ ሲያለቅስ ፡ እያዳፉ ፡
አወጡት ፡ ከሕዝቡም ፡ ጋር ፡ እስከ ፡ ባቢሎን ፡
ድረስ ፡ ወሰዱት ።
፳፪ ባሮክ ፡ ግን ፡ አመድ ፡ ዘግኖ ፡ በራሱ ፡ ነሰነሰ ፡
ተቀምጦም ፡ አለቀሰ ፡ ይህንንም ፡ ምሾ ፡ አሟሸ ።
፳፫ ስለ ፡ ተወደደ ፡ ስለ ፡ ሕዝቡ ፡ ኃጢአት ፡ ነው ፡
እንጂ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ስለምን ፡ ጠፋች ።
፳፬ ኃጥአን ፡ እንዳይታበዩ ፡ የፈጣሪንም ፡ አገር ፡
በኃይላችን ፡ መውረስ ፡ ተቻለን ፡ እንዳይሉ ፡
ኢየሩሳሌም ፡ በሕዝቡ ፡ ኃጢአትና ፡ በኛ ፡ ኃጢ
አት ፡ በጠላቶቿ ፡ እጅ ፡ ወደቀች ፡ እንጂ ፡
በነሱ ፡ ኃይል ፡ አይደለም ፡ አለ ።
፳፭ በኛ ፡ ኃጢአት ፡ ለናንተ ፡ ተሰጠቻችሁ ፡ እንጂ ፡
ይቺን ፡ አገር ፡ መውረስ ፡ የተቻላችሁ ፡ በናንተ ፡
ጽናት ፡ አይደለም ።
፳፮ ፈጣሪያችንም ፡ ያዝንልናል ፡ ወዳገራችንም ፡
ይመልሰናል ፡ ለናንተ ፡ ግን ፡ ድኅነት ፡ የላች
ሁም ።
፳፯ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ በሞት ፡ ወጥተው ፡ ሔደዋልና ፡
የዚችንም ፡ አገር ፡ መውረስ ፡ ጥፋት ፡ አላዩ
ምና ፡ አባቶቻችን ፡ ይስሐቅና ፡ አብርሃም ፡ ያዕ
ቆብ ፡ ንዑዳን ፡ ክቡራን ፡ ናቸው ።
ይህንንም ፡ ከተናገረ ፡ በኋላ ፡ እያለቀሰ ፡ ወጣ ፡ ኢየ ፳፰
ሩሳሌም ፡ ስላንቺ ፡ ኀዘንን ፡ አዝናለሁ ፡ አለ ።
ከከተማውም ፡ ወጥቶ ፡ በመቃብር ፡ ቤት ፡ አደረ ፡ ፳፱
መላእክትም ፡ መጥተው ፡ ሁሉን ፡ ይነግሩት ፡
ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

አቤሜሌክም ፡ ኤርምያስ ፡ ከላከው ፡ ቦታ ፡ ፩
በቀትር ፡ ጊዜ ፡ በለሱን ፡ አመጣ ፡ ጽፍቅ ፡ ያለች ፡
ዱርንም ፡ አገኘ ፡ ጥቂትም ፡ ያርፍ ፡ ዘንድ ፡ በጥ
ላዋ ፡ ስር ፡ ተቀመጠ ፡ በለስ ፡ ያለበትንም ፡
ሙዳዩ ፡ ተንተርሶ ፡ ስድሳ ፡ ስድስት ፡ ዓመት ፡
ተኛ ፡ ከመኝታውም ፡ አልነቃም ።
ከዚያ ፡ ዘመን ፡ በኋላ ፡ ከመኝታው ፡ ነቅቶ ፡ ፪
ተነሣ ፡ ገና ፡ ራሴን ፡ ይከብደኛልና ፡ እንቅል
ፌንም ፡ አልጨረስኩምና ፡ ዳግመኛ ፡ ጥቂት ፡
ብተኛ ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ ነው ፡ አለ ።
ያንጊዜም ፡ በለስ ፡ ያለበትን ፡ ሙዳዩ ፡ ከፈተ ፡ ፫
በለሶችም ፡ አዲስ ፡ ሁነው ፡ ወተታቸውም ፡
ሲፈስ ፡ አገኘ ፡ ራሱን ፡ ከብዶት ፡ ነበርና ፡ እንቅ
ልፉንም ፡ አልጨረሰምና ፡ ይተኛ ፡ ዘንድ ፡
ወደደ ።
ተመልሼ ፡ እንዳልተኛ ፡ እንዳልዘገይም ፡ እፈ ፬
ራለሁ ፡ አባቴ ፡ ኤርምያስ ፡ ተግቶ ፡ በጧት ፡
ልኮኛልና ፡ እንዳይነቅፈኝም ፡ እፈራለሁ ፡ አለ ።
ቀትር ፡ ሁኗልና ፡ በሁሉም ፡ የሚተውበት ፡ የለ ፭
ምና ፡ አሁንም ፡ ተነሥቼ ፡ እሄዳለሁ ፡ አለ ።
ተነሥቶ ፡ በለስ ፡ ያለበትን ፡ ሙዳዩ ፡ ይዞ ፡ ፮
ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ከተማ ፡ ገባ ። ከተማውን ፡
ቤቱንም ፡ አላወቀም ።
ጽኑ ፡ ድንጋጤ ፡ በሱ ፡ መጥቶበታልና ፡ አቤቱ ፡ ፯
አንተ ፡ የተመሰገንህ ፡ ነህ ፡ አለ ።
ይቺ ፡ አገር ፡ ኢየሩሳሌም ፡ አይደለችምን ፡ በተ ፰
ራራው ፡ ጎዳና ፡ መጥቻለሁና ፡ ራሴንም ፡ ከብ
ዶኛልና ፡ እንቅልፌንም ፡ አልጨረስኩምና ፡
አእምሮዬም ፡ ተዘንግቶኛልና ፡ ወይ ፡ እነሆ ፡
ተስቶኝ ፡ ይሆን ።
አገሪቱ ፡ በዕድ ፡ እንደ ፡ ሆነችብኝ ፡ በኤርም ፱
ያስ ፡ ዘንድ ፡ ይህንን ፡ ነገር ፡ እንዴት ፡ እናገራ
ለሁ ፡ አለ ፡ ኢየሩሳሌምም ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡
በገር ፡ ያለውን ፡ ምልክት ፡ ሁሉ ፡ ፈለገ ።
ዳግመኛ ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ ተመለሰ ፡ የሚአው ፲
ቀኝ ፡ እንዳለ ፡ ብሎ ፡ ፈለገ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ አላገ
ኘም ፡ ታላቅ ፡ ድንጋጤ ፡ በኔ ፡ መጥቶብኛልና ፡
አቤቱ ፡ አንተ ፡ የተመሰገንህ ፡ ነህ ፡ አለ ።
ሁለተኛ ፡ ከከተማ ፡ ርቆ ፡ ወጣ ፡ እያዘነም ፡ ተቀ ፲፩
ምጦ ፡ ሲሄድም ፡ ጎዳናውን ፡ አያውቅም ፡ ነበር ፡
በለስ ፡ ያለበትንም ፡ ሙዳዩ ፡ አኖረ ፡ ይህንን ፡
ድንቁርና ፡ እግዚአብሔር ፡ ከኔ ፡ እስኪያርቅ
ልኝ ፡ ድረስ ፡ በዚህ ፡ እቀመጣለሁ ፡ አለ ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ተቀምጦ ፡ ሳለ ፡ ሽማግሌ ፡ ሰው ፡ ፲፪

ከምድረ ፡ በዳ ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ ሲገባ ፡ አየ ።
፲፫ አቤሜሌክም ፡ አንተ ፡ ሽማግሌ ፡ ይቺ ፡ አገር ፡
ማናት ፡ ብዬ ፡ እጠይቅሃለሁ ፡ አለው ።
፲፬ ያም ፡ ሽማግሌ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ናት ፡ አለው ፡
ያገኘሁት ፡ ሰው ፡ የለምና ፡ የእግዚአብሔር ፡
አገልጋዩ ፡ ኤርምያስ ፡ የት ፡ አለ ፡ ባገር ፡ ያሉ ፡
መገኖች ፡ ሁሉና ፡ የሌዊ ፡ ወገን ፡ ባሮክስ ፡ የታሉ ፡
አለው ።
፲፭ ሽማግሌውም ፡ አንተ ፡ ከዚች ፡ አገር ፡ የተወለ
ድክ ፡ አይደለህምን ፡ ይህን ፡ ያህል ፡ ዘመን ፡
ኖረህ ፡ የሱን ፡ ነገር ፡ ትጠይቅ ፡ ዘንድ ፡ ኤርም
ያስን ፡ ዛሬ ፡ ማን ፡ አሰበው ፡ አለው ።
፲፮ ተማርከ ፡ በባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡ በናቡከደነፆር ፡
እጅ ፡ ተሰጥቷልና ፡ እስራኤልንም ፡ ያስተምር ፡
ዘንድ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ሄዷልና ፡ ኤርምያስስ ፡
ከሕዝቡ ፡ ጋር ፡ በባቢሎን ፡ አለ ፡ አለው ።
፲፯ አቤሜሌክም ፡ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ከዚያ ፡ ከሽማግ
ሌው ፡ ይህንን ፡ ቃል ፡ ሰማ ።
፲፰ አቤሜሌክም ፡ ሰውን ፡ ይልቁንም ፡ ሽማግሌ
ውን ፡ ሰው ፡ ሊንቁት ፡ አይገባም ፡ እንጂ ፡
አንተ ፡ ሽማግሌ ፡ ሰው ፡ ባትሆን ፡ በሰደብሁህ ፡
ነበር ፡ ባንተም ፡ በዘበትኩብህ ፡ ነበር ። ይህም ፡
ባይሆን ፡ አእምሮውን ፡ ያጣ ፡ ሽማግሌ ፡ ብዬ ፡
በሰደብሁህ ፡ ነበር ፡ አለው ።
፲፱ ሕዝቡ ፡ ተማርከው ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ሄዱ ፡ ስለም
ትለውስ ፡ ነገር ፡ የሰማይ ፡ ሻሻቴ ፡ ጦር ፡ በነሱ ፡
ቢወርድባቸው ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ተማርከው ፡
ይሄዱ ፡ ዘንድ ፡ ጊዜው ፡ አይደለም ፡ አለው ።
፳ አንተ ፡ ግን ፡ ተማርከው ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ሔዱ ፡
ትላለህ ፡ በሕዝቡ ፡ ዘንድ ፡ ላሉ ፡ ለበሽተኞች ፡
እንዕጥ ፡ ዘንድ ፡ አባቴ ፡ ኤርምያስ ፡ እኔን ፡ እን
ደላከኝ ፡ ጥቂት ፡ በለስ ፡ ላመጣ ፡ ወደ ፡ አግሪ
ጳስ ፡ ወይን ፡ ቦታ ፡ ሔድኩ ፡ አለ ።
፳፩ ሔጄም ፡ ከዚያ ፡ ደረስኩ ፡ ያዘዘኝንም ፡ ይዤ ፡
ተመለስኩ ፡ ስሔድም ፡ አንዲት ፡ እንጨትን ፡
አገኘሁ ፡ የቀትር ፡ ጊዜ ፡ ነበርና ፡ በበታቿ ፡
አርፍ ፡ ዘንድ ፡ ተቀመጥኩ ።
፳፪ ከዚያም ፡ በለስ ፡ ያለበትን ፡ሙዳይ ፡ ተንተ
ርሼ ፡ ተኛሁ ፡ ከንቅልፌም ፡ በነቃሁ ፡ ጊዜ ፡
የዘገየሁ ፡ መሰለኝ ፡ በለስ ፡ ያለበትን ፡ ይኸንን ፡
ሙዳይ ፡ ከፍቼ ፡ አየሁ ፡ መርጬ ፡ እንደለቀም
ኋቸው ፡ ወተቱ ፡ ሲፈስ ፡ አገኘሁት ።
፳፫ አንተ ፡ እነሆ ፡ ሕዝቡ ፡ ተማርከው ፡ ወደ ፡ ባቢ
ሎን ፡ ሔዱ ፡ ትላለህ ፡ እነሆ ፡ በለሱ ፡ እንዳልጠ
ወለገ ፡ እይ ፡ ብሎ ፡ በለስ ፡ ያለበትን ፡ ሙዳይ ፡
ከፍቶ ፡ አሳየው ።
፳፬ ሽማግሌውም ፡ በለሱ ፡ አዲስ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
ወተቱም ፡ እንዲፈስ ፡ አይቶ ፡ ያንጊዜ ፡ ያ ፡ ሽማ
ግሌ ፡ አደነቀ ።
፳፭ አቤሜሌክንም ፡ ልጄ ፡ አንተ ፡ ደግ ፡ ሰው ፡
ነህ ፡ ፈጣሪህ ፡ የዚችን ፡ አገር ፡ ጥፋት ፡ ሊያሳ
ይህ ፡ አልወደደምና ፡ ላንተ ፡ ፈጣሪህ ፡ መረጋጋ
ትን ፡ (እንቅልፍ ፡ ) አምጥቶ ፡ አዳነህ ፡ አለው ።
፳፮ ሕዝቡ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ተማርከው ፡ ከሔዱ ፡
እነሆ ፡ ዛሬ ፡ ስድሳ ፡ ስድስት ፡ ዓመት ፡ ሆነ ።
ልጄ ፡ ፈጽመህ ፡ ልታውቅስ ፡ ከወደድክ ፡ ዘሮቹ ፡ ፳፯
እንዳለቀሱ ፡ ወደርሻዎች ፡ ፈጽመህ ፡ ተመል
ከት ፡ የበለስ ፡ ግን ፡ ጊዜው ፡ አይደለም ፡ አለው ፡
የዚያን ፡ ጊዜ ፡ አቤሜሌክ ፡ የዚህ ፡ ሁሉ ፡
ጊዜው ፡ እንዳልሆነ ፡ አወቀ ።
ቃሉን ፡ አሰምቶ ፡ ምድርና ፡ ሰማይን ፡ የፈጠ ፳፰
ርህ ፡ ፈጣሪዬ ፡ ጌታዬ ፡ አመሰግንሃለሁ ፡ በየ
ሀገሩ ፡ ሁሉ ፡ ለጻድቃንም ፡ ነፍሶች ፡ ዕረፍ
ታቸው ፡ አንተ ፡ ነህ ፡ አለ ።
ሽማግሌውንም ፡ ይህ ፡ ወር ፡ ማነው ፡ አለው ፡ ፳፱
የኔሳን ፡ ወር ፡ አሥራ ፡ ሁለተኛው ፡ ቀን ፡ ነው ፡
ይኸውም ፡ ሚያዝያ ፡ ነው ፡ አለው ።
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ አቤሜሌክ ፡ ለዚህ ፡ ሽማግሌ ፡ ፴
ከነዚህ ፡ በለሶች ፡ ሰጠው ፡ ፈጣሪህ ፡ ወደ ፡
ኢየሩሳሌም ፡ ሰማያዊት ፡ አገር ፡ ይምራህ ፡
አለው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

አቤሜሌክም ፡ ተነሥቶ ፡ ከከተማ ፡ ወደ ፡ ፩
ውጪ ፡ ከወጣ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
ለመነ ።
እነሆ ፡ መልአክ ፡ መጥቶ ፡ ወደ ፡ ባሮክ ፡ መርቶ ፡ ፪
ወሰደው ፡ በመቃብር ፡ ቤትም ፡ ተቀምጦ ፡
አገኘው ።
እጅ ፡ በተነሣው ፡ ጊዜ ፡ እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ተለ ፫
ቃቅሰው ፡ ተሳሳሙ ፡ በሙዳዩም ፡ ውስጥ ፡
በለሱን ፡ አይቶ ፡ ዓይኖቹን ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡
አቅንቶ ።
ለወዳጆቹ ፡ ለጻድቃን ፡ ዋጋቸውን ፡ የሚሰጣ ፬
ቸው ፡ ፈጣሪ ፡ ገናና ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ጸለየ ፡
ነፍሴ ፡ ተዘጋጂ ፡ ለከበረ ፡ ለማደሪያሽ ፡ በሥጋ ፡
ይህነን ፡ እየነገርሽ ፡ ደስ ፡ ይበልሽ ፡ ልቅሶሽም ፡
ወደ ፡ ደስታ ፡ ይመለስልሻል ፡ አለ ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ የታመነ ፡ ክርስቶስ ፡ ይመጣል ፡ ፭
ወደ ፡ ሬሳሽም ፡ ይመልስሻል ፡ መጠርጠር ፡ ወደ
ሌለው ፡ ሃይማኖትሽም ፡ ተመልከች ።
ወተታቸው ፡ ገና ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ይፈሳል ፡ ፮
እንጂ ፡ እነሆ ፡ እኒህ ፡ በለሶች ፡ ከተለቀሙ ፡ ስድሳ ፡
ስድስት ፡ ዓመት ፡ ነው ፡ አልጠፉም ፡ አልተሉም ፡
አልሸተቱም ፡ ይህንም ፡ በለስ ፡ ዓይተሽ ፡ አን
ቺም ፡ እንድትነሺ ፡ እመኚ ።
ኃጢአት ፡ የለብሽምና ፡ በለስ ፡ ያለበትን ፡ ፯
ሙዳይ ፡ ከጠበቀ ፡ ከውነተኛ ፡ መልአክ ፡ ዘንድ ፡
የታዘዝሺውን ፡ ትእዛዝም ፡ ጠብቀሻልና ፡
ሥጋዬ ፡ ባንቺ ፡ እንዲህ ፡ ያደርጋል ፡ እሱም ፡
ዳግመኛ ፡ ኃይሉ ፡ ይጠብቅሻል ፡ አለ ።
ባሮክ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ከጸለየ ፡ በኋላ ፡ አቤሜ ፰
ሌክ ፡ መለሰ ፡ እኔን ፡ የሠወረ ፡ እግዚአብሔር ፡
ለኤርምያስ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ የምንጽፋቸውን ፡
ቃሎች ፡ ይገልጥልን ፡ ዘንድ ፡ ዳግመኛ ፡ ተነሥ
ተህ ፡ ጸልይ ፡ አለው ።
ባሮክም ፡ ኃይለኛ ፡ ፈጣሪ ፡ ብርሃንም ፡ ከፍህ ፡ ፱
የሚወጣ ፡ አቤቱ ፡ እለምንህ ፡ ዘንድ ፡ እወዳ

ለሁ ፡ ብሎ ፡ ለመነ ።
፲ ለቸርነትህም ፡ እገዛለሁ ፡ ስምህም ፡ ገናና ፡ ነው ፡
እሱንም ፡ መርምሮ ፡ ማወቅ ፡ የሚቻለው ፡
የለም ።
፲፩ በልቡናዬ ፡ ፈቃድህን ፡ ለማድረግ ፡ በደግነት ፡
የታወቅሁ ፡ እሆን ፡ ዘንድ ፡ ላገልጋይህ ፡ ለኤር
ምያስም ፡ ወደ ፡ በቢሎን ፡ ጽፎ ፡ እሰድ ፡ ዘንድ ፡
የኔን ፡ የበሪያህን ፡ ልመና ፡ ስማ ፡ አለ ።
፲፪ ይህነን ፡ ሲጸልይ ፡ መልአኩ ፡ ወጥቶ ፡ የዕውቀትን ፡
ነገር ፡ የምትመክር ፡ ባሮክ ፡ አንተ ፡ ወደ ፡ ኤር
ምያስ ፡ ትልክ ፡ ዘንድ ፡ ማንን ፡ እልክለሁ ፡ ብለህ ፡
አታስብ ፡ አለው ።
፲፫ ነገ ፡ ፀሐይ ፡ ሲወጣ ፡ ንስር ፡ ወዳንተ ፡ ይመ
ጣል ፡ ወደ ፡ ኤርምያስ ፡ የምትልከውን ፡ ነገር ፡
አንተ ፡ መርምር ፡ በመጽሐፉም ፡ ጻፍ ፡ አለው ።
፲፬ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ እንዲህ ፡ በላቸው ፡ በና
ንተ ፡ ዘንድ ፡ እንግዳ ፡ ሰው ፡ ቢኖር ፡ እስከ ፡
አሥራ ፡ ምስት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ከናንተ ፡ ይለዩ ፡
በላቸው ።
፲፭ እግዚአብሔርም ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ አገራ
ችሁ ፡ አገባችኋለሁ ፡ አለ ፡ እስከ ፡ አሥራ ፡ አም
ስት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ከባቢሎን ፡ ያልተለየ ፡ ሰው ፡
እግዚአብሔር ፡ ኤርምያስ ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ ገብቶ ፡
በባቢሎን ፡ ያሉ ፡ እስራኤልን ፡ ይገለፋቸው ፡
አሉ ።
፲፮ ይህነንም ፡ ከተናገረ ፡ በኋላ ፡ መልአኩ ፡ ከባ
ሮክ ፡ ዘንድ ፡ ሄደ ። ባሮክም ፡ እስከደባበዩ ፡
ድረስ ፡ ሸኘው ፡ ወረቀቱን ፡ ጥቁር ፡ ቀለም ፡
አምጥቶ ።
፲፯ ስለ ፡ ጥፋታችንና ፡ ስለ ፡ ስድባችን ፡ ያዘንን ፡
ሆነን ፡ እንወጣ ፡ ዘንድ ፡ ፈጣሪያችን ፡ አልተወ
ንምና ፡ የእግዚአብሔር ፡ አገልጋዩ ፡ ባሮክ ፡
ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ለተማረከ ፡ ለኤርምያስ ፡ ተድላ ፡
ደስታውን ፡ በመጽሐፍ ፡ እጽፋለሁ ፡ ብሎ ፡
ደብዳቤ ፡ ጻፈ ።
፲፰ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ጌታችን ፡ እንባችንን ፡ አይቶ ፡
አዘነልን ፡ አስቀድሞ ፡ ላባቶቻችን ፡ ለይስሐቅና ፡
ለአብርሃም ፡ ለያዕቆብ ፡ የሠራውን ፡ ሥርዓት ፡
አሰበ ።
፲፱ መልአኩንም ፡ ወደኔ ፡ ልኮ ፡ ወዳንተ ፡ የላክሁ
ብህን ፡ ነገሮች ፡ ነገረኝ ።
፳ ከፈርዖን ፡ አገዛዝና ፡ ከግብፅ ፡ አገር ፡ ያወጣን ፡
የእስራኤል ፡ ፈጣሪ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያደረጋ
ቸው ፡ ነገሮች ፡ እኒህ ፡ ናቸው ፡ ልቡናችሁን ፡
በትዕቢት ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረጋችሁ ፡ እንጂ ፡
በፊቱም ፡ ክፉደ ፡ ልቡናችሁን ፡ አጸናችሁ ፡
እንጂ ፡ ሕጉን ፡ ሁሉ ፡ አልጠበቃችሁምና ።
፳፩ እግዚአብሔር ፡ ከወዳጁ ፡ ከኤርምያስ ፡ አፍ ፡
ቃሉን ፡ አልሰማችሁም ፡ ብሏልና ፡ ለባቢሎን ፡
አገዛዝ ፡ አሳልፎ ፡ ሰጣችሁ ፡ ቃሉን ፡ የሰሙ ፡
ሰዎችን ፡ ግን ፡ ከባቢሎን ፡ አወጣቸዋለሁ ፡ ከባ
ቢሎንም ፡ ወጥተው ፡ በኢየሩሳሌም ፡ እንግዳ ፡
አይሆኑም ።
፳፪ ሥራቸውንም ፡ ልታውቅባቸው ፡ ብትወድ ፡
በዮርዳኖስ ፡ ውኃ ፡ ፍተናቸው ፡ የዚህን ፡ ደብ
ዳቤ ፡ ምልክት ፡ ያልሰማ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ የበለጠ ፡
ምልክት ፡ ማንትም ፡ አለ ። ( የምውት ፡ መነ
ሣት ፡ )
ባሮክ ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ጽሕፈት ፡ ጽፎ ፡ ከመቃ ፳፫
ብር ፡ ቤት ፡ ወጣ ፡ ንስሩም ፡ ሃይማኖትን ፡ የም
ታስተምር ፡ ባሮክ ፡ ቸር ፡ አለህ ፡ አለው ።
ባሮክም ፡ ከሰማይ ፡ አዕዋፍ ፡ ሁሉ ፡ የተመረ ፳፬
ጥክ ፡ አንተ ፡ ትናገራለህና ፡ በዩናችህ ፡ ብርሃን ፡
የታወቅህ ፡ ነህ ።
አሁንም ፡ በዚህ ፡ ምን ፡ ልታደርግ ፡ መጣህ ፡ ፳፭
ንገረኝ ፡ አለው ፡ ንስርም ፡ የወደድኸውን ፡
ሁሉ ፡ እኔን ፡ ልትልከኝ ፡ ወደዚህ ፡ መጣሁ ፡
አለው ።
ባሮክም ፡ እሊህን ፡ ነገሮች ፡ ለኤርምያስ ፡ ወደ ፡ ፳፮
ባቢሎን ፡ ማድረስ ፡ ይቻልሃልን ፡ አለው ፡ ንስ
ርም ፡ ስለዚህ ፡ ተላክሁ ፡ አለው ።
ባሮክም ፡ ደብዳቤውን ፡ ያዝ ፡ ከዚያ ፡ አቤሜ ፳፯
ሌክ ፡ ከሰጠው ፡ ከበለሱ ፡ ሙዳይም ፡ አሥራ ፡
አምስቱን ፡ በለስ ፡ አምጥቶ ፡ በንስሩ ፡ አንገት ፡
ቋጠረ ።
የአዕዋፍ ፡ ሁሉ ፡ ንጉሣቸው ፡ ንስር ፡ በፍቅር ፡ ፳፰
በተድላ ፡ በደስታ ፡ ሒደህ ፡ ወሬያቸውን ፡ አም
ጣልን ፡ እልሃለሁ ፡ አለው ።
ለኖኅ ፡ ቃሏን ፡ ሶስት ፡ ጊዜ ፡ የመለሰች ፡ ርግ ፳፱
ብን ፡ ምሰላት ፡ እንጂ ፡ ኖኅ ፡ የላከው ፡ ዳግመኛ ፡
ወደሱ ፡ መመለስን ፡ እምቢ ፡ ያለ ፡ ቁራን ፡ አት
ምሰለው ።
እንደዚህም ፡ ሁሉ ፡ አንተ ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ ይሆ ፴
ንህ ፡ ዘንድ ፡ እኒህን ፡ ያማሩ ፡ ነገሮች ፡ ለኤርም
ያስ ፡ ከሱም ፡ ጋራ ፡ ላሉ ፡ እስራኤል ፡ ውሰድ ፡
አምላክ ፡ ለመረጣቸውም ፡ ወገኖች ፡ ይህን ፡
ተድላ ፡ ደስታ ፡ ንገራቸው ።
አዕዋፍም ፡ ሁሉ ፡ ቢከቡህ ፡ ይገድሉህ ፡ ዘንድ ፡ ፴፩
ወደው ፡ የሃይማኖት ፡ ጠላቷም ፡ ሁሉ ፡ ቢከ
ቡህ ፡ በሃይማኖትህ ፡ ቀድመሃቸው ፡ ሒድ ።
ጌታም ፡ ኃይልን ፡ ይሰጥሃል ፡ የተወረወረ ፡ ፴፪
ፍላፃ ፡ ቀንቶ ፡ እንዲሒድ ፡ አንተም ፡ በፈጣ
ሪህ ፡ ኃይል ፡ ቀንተህ ፡ ሒድ ፡ እንጂ ፡ ወደ ፡
ቀኝም ፡ ወደ ፡ ግራም ፡ አትመለስ ፡ አለው ።

ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

ባሮክ ፡ ይህን ፡ ከተናገረ ፡ በኋላ ፡ ንስር ፡ መጽ ፩
ሐፉን ፡ ይዞ ፡ በረረ ፡ ወደ ፡ ባቢሎንም ፡ ሔዶ ፡
በምድረ ፡ በዳ ፡ ባለው ፡ ቦታ ፡ ከከተማ ፡ በአ
ፍዓ ፡ ባለ ፡ ምሰሶ ፡ ላይ ፡ አረፈ ።
ኤርምያስ ፡ እስኪያልፍ ፡ ድረስ ፡ ሌሎቹም ፡ ፪
ወገኖች ፡ እስኪያልፉ ፡ ድረስ ፡ በዚያው ፡ ቆየ ፡
ኤርምያስ ፡ ናቡከደነፆርን ፡ ከወገኖቹ ፡ የሞተ
ውን ፡ የምቀብርበት ፡ ቦታ ፡ስጠኝ ፡ ብሎ ፡ ለም
ኗልና ፡ ናቡከደነፆርም ፡ ሰጥቶታልና ፡ ሕዝቡ ፡
የሞተውን ፡ ሰው ፡ ሊቀብሩ ፡ ወደዚያ ፡ ቦታ ፡
ሔዱ ።
ለሞተውም ፡ ሰው ፡ እያለቀሱ ፡ ሲሄዱ ፡ ከን ፫

ስሩ ፡ ፊት ፡ ደረሱ ።
፬ በዚያም ፡ ቦታ ፡ ሆኖ ፡ በታላቅ ፡ ቃል ፡ አሰምቶ ፡
ራሱኽ ፡ አምላክ ፡ የመረጠህ ፡ ኤርምያስ ፡ ላንተ ፡
እንግርሃለሁ ፡ ሂደህ ፡ ሕዝቡን ፡ ሁሉ ፡ ሰብስበ
ቸው ፡ እኔ ፡ ያመጣሁትን ፡ በጎ ፡ የምስራች ፡
እስኪሰሙ ፡ ድረስ ፡ ወደዚህ ፡ ይምጡ ፡ አለው ።
፭ ኤርምያስም ፡ ይህንን ፡ ሰምቶ ፡ እግዚአብሔርን ፡
አመሰገነው ፡ ያን ፡ ጊዜም ፡ ሕዝቡን ፡ ሁሉ ፡ ልጆ
ቻቸውንና ፡ ሚስቶቻቸውንም ፡ ሰበሰበ ፡ እነ
ሱም ፡ ንስሩ ፡ ወዳለበት ፡ ደረሱ ።
፮ ንስሩም ፡ ሬሳው ፡ ወዳለበት ፡ ወርዶ ፡ ረገጠው ፡
ሙቱም ፡ ተነሣ ፡ ይህንንም ፡ ያደረገ ፡ ስለ ፡ ተደ
ረገላቸው ፡ ታምራት ፡ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ያምኑ ፡
ዘንድ ፡ ያደንቁም ፡ ዘንድ ፡ ነው ።
፯ ከሙሴ ፡ ጋር ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ላሉ ፡ ላባቶቻ
ችን ፡ የታያቸው ፡ ፈጣሪያችን ፡ እነሆ ፡ ይህ ፡
እንደ ፡ ሆነ ፡ ዛሬም ፡ በታላቅ ፡ ንስር ፡ አምሳል ፡
ለኛ ፡ የታየን ፡ ይህ ፡ ነው ፡ አሉ ።
፰ ንስርም ፡ ኤርምያስን ፡ መጥተህ ፡ ይህንን ፡ መጽ
ሐፍ ፡ ስማ ፡ ለሕዝቡም ፡ አንብብላቸው ፡ አለው ፡
እሱም ፡ ለሕዝቡ ፡ አነበበላቸው ።
፱ ሕዝቡም ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ሁሉም ፡ አንድ ፡ ሆነው ፡
አለቀሱ ፡ በራሳቸውም ፡ አመድ ፡ ነሰነሱ ፡ ኤር
ምያስንም ፡ ወዳገራችን ፡ እንገባ ፡ ዘንድ ፡ ምን ፡
እንሥራ ፡ ንገረን ፡ አሉት ።
፲ ኤርምያስም ፡ ተነሥቶ ፡ በደብዳቤ ፡ የሰማችሁ
ትን ፡ ሁሉ ፡ እንደዚሁ ፡ አድርጉ ፡ ወዳገራችሁ ፡
ይመልሳችኋል ፡ አላቸው ።
፲፩ ኤርምያስም ፡ ለባሮክ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ደብ
ዳቤ ፡ ጻፈ ፡ በኃጢአተኛ ፡ ንጉሥ ፡ በዳርዮስ ፡
ትእዛዝ ፡ እስክንወጣ ፡ ድረስ ፡ ይቅር ፡ ይለን ፡
ዘንድ ፡ ወደ ፡ ጎዳናችንም ፡ ይመራን ፡ ዘንድ ፡
ስለኛ ፡ ፈጣሪያችንን ፡ እየተለማመጥክ ፡ መለ
መኑን ፡ ቸል ፡ አትበል ።
፲፪ አንተ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ተማርከው ፡ ከመጡ ፡
ወገኖች ፡ ጋራ ፡ ልትመጣ ፡ ባልተወህ ፡ በፈጣ
ሪህ ፡ ፊት ፡ ባለሟልነትን ፡ አገኘህ ።
፲፫ አንድ ፡ ልጅ ፡ እንዳለው ፡ አባት ፡ ይሞት ፡ ዘንድ ፡
እሱ ፡ ለሞት ፡ እንደ ፡ ተሰጠ ፡ የሚያላቅሱት ፡
በባቱ ፡ ዘንድ ፡ ያሉት ፡ ሰዎች ፡ አባቱ ፡ በኃዘን ፡
ጥርሱን ፡ ሲያገጥ ፡ ዓይኑን ፡ ሲያፈጥ ፡ እንዳያ
ዩት ፡ ፊታቸውን ፡ እንዲሸፍኑ ።
፲፬ እንደዚሁ ፡ ፈጣሪህ ፡ አንተን ፡ ይቅር ፡ አለህ ፡
እኛ ፡ ወደዚህ ፡ አገር ፡ ከደረስን ፡ ጀምሮ ፡ ዛሬ ፡
ከኃዘን ፡ አላረፍንምና ፡ የሕዝቡን ፡ መከራ ፡
እንዳታይ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ትመጣ ፡ ዘንድ ፡
አልተወህም ።
፲፭ እያለቀሱ ፡ አቤቱ ፡ የሰሮት ፡ አምላክ ፡ ይቅር ፡
በለን ፡ እያሉ ፡ ከንጉሡ ፡ ከናቡከደነፆር ፡ መከራ ፡
ከተቀበሉ ፡ ወገኖች ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ እናገኝ ፡
ዘንድ ፡ ስንፈልግ ፡ ዛሬ ፡ ስሳ ፡ ስድስት ፡ ዓመት ፡
ነው ፡ አሉ ።
፲፮ እኒህ ፡ ያዘኑ ፡ ሰዎች ፡ ሌላውን ፡ አምላክ ፡ ሲጠሩ ፡
ይቅር ፡ በለንም ፡ ሲሉ ፡ ይህንን ፡ ነገር ፡ በሰማሁ ፡
ጊዜ ፡ አገዥ ፡ አለቀስኩ ።
፲፯ ዳግመኛም ፡ እኔ ፡ ስንማረክ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ያደ
ረግነውን ፡ በዓል ፡ አሰብኩ ፡ ይህንንም ፡ አስቤ ፡
እየተጨነቅሁ ፡ እያለቀስኩ ፡ ወደ ፡ ቤቴ ፡ እመ
ለሳለሁ ።
፲፰ አሁንም ፡ ከፋርስ ፡ አገር ፡ እንዲወጡ ፡ ቃሉን ፡
ይሰሙ ፡ ዘንድ ፡ ከፊ ፡ የወጣውንም ፡ ነገር ፡ ይቀ
በሉ ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ወገኖቻችን ፡ አቤሜሌክና ፡
አንተ ፡ በላችሁበት ፡ ቦታ ፡ ፈጣሪያችንን ፡
ለምኑ ።
፲፱ አሁንም ፡ በኖርንበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ፈጣሪያ
ችሁ ፡ በጽዮን ፡ ከሚመሰገነው ፡ ምስጋና ፡ ወገን ፡
አዲስ ፡ ምስጋናን ፡ ንገሩን ፡ ብለው ፡ ያዙን ፡
ብዬ ፡ እነግርሃለሁ ።
፳ እኛም ፡ በባዕድ ፡ አገር ፡ ስለን ፡ እንደ ፡ ምን ፡
እናመሰግንላችኋለን ፡ አልናቸው ።
፳፩ ኤርምያስም ፡ እንደዚሁ ፡ አድርጎ ፡ ጽፎ ፡ ደብ
ዳቤውን ፡ በንስሩ ፡ አንገት ፡ ዳጠረ ፡ በፍቅር ፡
ሂድ ፡ ጌታም ፡ አንተን ፡ በረድኤት ፡ ይጐብኝ ፡
አለው ።
፳፪ ንስሩም ፡ ደብዳቤውን ፡ ይዞ ፡ በሮ ፡ ሔደ ፡ ደብ
ዳቤውንም ፡ ወደ ፡ ባሮክ ፡ አደረሰ ፡ ባሮክም ፡
ደብዳቤውን ፡ አንሥቶ ፡ አነበበው ፡ የሕዝቡን ፡
ኃዘን ፡ መከራቸውንም ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ አለቀሰ ።
፳፫ ኤርምያስ ፡ ግን ፡ ያንን ፡ በለስ ፡ ተቀብሎ ፡ በሕ
ዝቡ ፡ ዘንድ ፡ ላሉ ፡ በሽተኞች ፡ ሰጣቸው ።
፳፬ የባቢሎንን ፡ ወገኖች ፡ ሥራ ፡ እንዳይሠሩ ፡ እያ
ስተማራቸው ፡ ተቀመጠ ።
፳፭ እግዚአብሔር ፡ ሕዝቡን ፡ ከባቢሎን ፡ በሚያ
ወጣ ፡ ገንዘብ ፡ የሚያወጣበት ፡ ቀን ፡ በደረሰች ፡
ጊዜ ።
፳፮ ጌታ ፡ ኤርምያስን ፡ አንተ ፡ ተነሥ ፡ ወገኖችህም ፡
ይነሡ ፡ ወደ ፡ ዮርዳኖስም ፡ ኑ ፡ አለው ፡ ሕዝቡ
ንም ፡ ጌታ ፡ የባቢሎንን ፡ ወገኖች ፡ ሥራ ፡
ይተው ፡ ዘንድ ፡ ይወዳል ፡ በላቸው ።
፳፯ ከናንተ ፡ ሴቶችን ፡ ያገባ ፡ ወንድን ፡ ወንዶችን ፡
ያገቡ ፡ ሴቶችንም ፡ ፍቱናቸው ፡ አለው ፡ ቃል
ህን ፡ የሰሙ ፡ ሰዎችን ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡
መልሳቸው ፡ ያልሰሙህን ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ወደዚ ፡
ይገቡ ፡ ዘንድ ፡ አትተዋቸው ፡ አለው ።
፳፰ ኤርምያስም ፡ እንደዚሁ ፡ ይህንን ፡ ሁሉ ፡ አነበ
በላቸው ፡ ሊመረምራቸውም ፡ ወደ ፡ ዮርዳኖስ ፡
አመጣቸው ፡ ጌታ ፡ ያላቸውን ፡ ይህንንም ፡ ነገር ፡
ሲነግራቸው ፡ ያገቡ ፡ ሰዎች ፡ ተጠራጠሩ ፡ ሊፋ
ቱም ፡ አልወደዱም ፡ ኤርምያስንም ፡ ይሰሙት ፡
ዘንድ ፡ ስሙት ፡ ብሎ ፡ አዘዛቸው ።
፳፱ ምሽቶቻችንን ፡ ለዘለዓለሙ ፡ አንተውም ፡ ከኛ ፡
ጋሬ ፡ ወዳገራችን ፡ እንወስዳቸዋለን ፡ ያሉ ፡
ሰዎች ፡ አሉ ፡ ከዮርዳኖስም ፡ አልፈው ፡ ወደ ፡
ኢየሩሳሌም ፡ ደረሱ ።
፴ ኤርምያስ ፡ አቤሜሌክና ፡ ባሮክም ፡ ከባቢሎን ፡
ሴት ፡ ያገባ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ወዳገራችን ፡ አይገ
ባም ፡ ብለው ፡ በጠላትነት ፡ ተነሡባቸው ።
፴፩ ምሽት ፡ ያገቡ ፡ ሰዎችም ፡ ባልንጀሮቻቸውን ፡

ተነሡ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ እንመለስ ፡ አሏቸው ፡
ወደ ፡ ባቢሎንም ፡ ተመልሰው ፡ ሄዱ ።
፴፪፤ የባቢሎንም ፡ ሰዎች ፡ ባዩዋቸው ፡ ጊዜ ፡ ሊቀበ
ሏቸው ፡ ወጡ ፡ እናንተ ፡ አስቀድማችሁ ፡ እኛን ፡
ጠልታችሁናልና ፡ ከኛ ፡ ተሠውራችሁ ፡ ወጣ
ችሁ ፡ ብለው ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ ይገቡ ፡ ዘንድ ፡
አልተዋቸውም ።
፴፫፤ ከኛ ፡ ተሠውራችሁ ፡ ስለ ፡ ወጣችሁ ፡ ሴቶች ፡
ልጆቻችሁንና ፡ እናንተን ፡ እንዳንቀበላችሁ ፡
በፈጣሪያችን ፡ ስም ፡ ምለናልና ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡
በደላችሁ ፡ ወዳገራችን ፡ አትገቡም ፡ አሏቸው ።
፴፬፤ እንደዚህ ፡ ያለውን ፡ ቃል ፡ ሰምተው ፡ ወደ ፡
ኢየሩሳሌም ፡ ተመለሱ ፡ በኢየሩሳሌምም ፡
አውራጃ ፡ አገር ፡ አቀኑ ፡ ያንንም ፡ አገር ፡ ሰማ
ርያ ፡ አሉት ።
፴፭፤ ኤርምያስም ፡ ንስሐ ፡ ግቡ ፡ ብሎ ፡ ወደነሱ ፡
ላከ ፡ እነሆ ፡ በውነት ፡ የተሾመ ፡ ዘሩባቤል ፡ ይመ
ጣል ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ ወደምትኖሩበት ፡ በታች
ሁም ፡ ይመልሳችኋል ፡ አላቸው ፡ እነሱም ፡
ደስ ፡ ብሏቸው ፡ ስለ ፡ ሕዝቡ ፡ መሥዋዕት ፡
እየሠዉ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ተቀመጡ ።
፴፮፤ ይህ ፡ ከተደረገ ፡ በኋላ ፡ አሥር ፡ ቀን ፡ በሆን ፡
ጊዜ ፡ ኤርምያስ ፡ ብቻውን ፡ ወጣ ።
፴፯፤ ኤርምያስም ፡ ለሰው ፡ በጎ ፡ መዓዛ ፡ የምትሆን ፡
አንተ ፡ ንጹሕ ፡ ክቡር ፡ ልዩ ፡ ነህ ፡ ወዳንተም ፡
እስክደርስ ፡ ድረስ ፡ ሰውቀትን ፡ የምትገልጥ
ልኝ ፡ እውነተኛ ፡ አዋቂ ፡ አንተ ፡ ነህ ፡ ብሎ ፡
ለመነ ።
፴፰፤ ስለ ፡ ወገኖችህ ፡ ስለ ፡ እስራኤልም ፡ አለምንሃ
ለሁ ፡ ስለተወደደ ፡ ስለ ፡ ሱራፌል ፡ ምስጋና ፡
በጎ ፡ መዓዛ ፡ ስላለው ፡ ስለ ፡ ኪሩቤልም ፡ ሰማን ፡
እለምንሃለሁ ፡ ለውነት ፡ ነገር ፡ የሚላክ ፡ ሚካ
ኤልም ፡ በውነት ፡ አመስጋኝ ፡ ነው ፡ እውቀ
ቱን ፡ የሚገልጥልኝ ፡ ጻድቃን ፡ እስከ ፡ ገቡባ
ቸው ፡ ድረስ ፡ የውነት ፡ በሮቹን ፡ የሚከፍትልኝ ፡
እሱ ፡ ነው ።
፴፱፤ የሁሉ ፡ ጌታ ፡ አቤቱ ፡ አለምንሃለሁ ፡ ሁሉን ፡
የምትገዛ ፡ ጌታ ፡ አንተ ፡ ነህ ፡ የሚታየውን ፡
ሁሉ ፡ የማይታየውንም ፡ ፈጥሮ ፡ ጨረሰ ፡ የተ
ሠወረው ፡ ሁሉ ፡ ሳይፈጠርም ፡ ተሠውሮ ፡ የነ
በረው ፡ ሁሉ ፡ በሱ ፡ ዘንድ ፡ አለ ።
፵፤ ይኸንን ፡ ጸሎት ፡ ጸልዩ ፡ ልመናውንም ፡ ከጨ
ረሰ ፡ በኋላ ፡ ኤርምያስ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡
ገብቶ ፡ ቆመ ፡ አቤሜሌክና ፡ ባሮክም ፡ ከሱ ፡
ጋራ ፡ ነበሩ ፡ ኤርምያስም ፡ ነፍሱ ፡ ከሥጋው ፡
እንደ ፡ ተለየች ፡ እንደ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ሆነ ።
፵፩፤ ያን ፡ ጊዜም ፡ አቤሜሌክና ፡ ባሮክ ፡ ወድቀው ፡
ቃላቸውን ፡ አሰምተው ፡ ጮሁ ፡ የፈጣሪያችን ፡
አገልጋይ ፡ አባታችን ፡ ኤርምያስ ፡ ከኛ ፡ ተለ
ይቶ ፡ ሞተ ፡ ወዮልን ፡ አሉ ።
፵፪፤ ሕዝቡም ፡ እንዲህ ፡ ሲሉ ፡ ሰምተው ፡ ወደሱ ፡
ሮጡ ፡ ኤርምያስንም ፡ ሞቶ ፡ ወድቆ ፡ አገኙት ፡
ልብሶቻቸውንም ፡ ቀደዱ ፡ በራሳቸውም ፡ ትቢያ ፡
ነሰነሱ ፡ የሚያሳዝን ፡ ልቅሶንም ፡ አለቀሱ ።

የሚቀብሩበትን ፡ መግነዝ ፡ ከዘጋጁ ፡ በኋላ ፡ ፵፫፤
ደኅና ፡ ነውና ፡ ነፍሱም ፡ ዳግመኛ ፡ ወደ ፡
ሥጋው ፡ ትመለሳለችና ፡ አትገንዙት ፡ የሚል ፡
ቃል ፡ መጣ ።
ይህንንም ፡ ቃል ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ዳግመኛ ፡ ነፍሱ ፡ ፵፬፤
ወደ ፡ ሥጋው ፡ እስክትመለስ ፡ ድረስ ፡ እየጠበ
ቁት ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ በዙሪያው ፡ ተቀመጡ ፡
እንጂ ፡ ይህን ፡ አልገነዙትም ።
በሁሉም ፡ መካከል ፡ ቃል ፡ ተሰማ ፡ ፈጣሪያች ፵፭፤
ንን ፡ በንድ ፡ ቃል ፡ አመስግኑት ፡ የሚያስነሣ
ችሁ ፡ የአብ ፡ ልጅ ፡ ወልድንም ፡ ሁላችሁ ፡ አመ
ስግኑት ።
የዓለሙ ፡ ሁሉ ፡ ብርሃን ፡ የሚሆን ፡ የአብ ፡ ልጅ ፡ ፵፮፤
ኢየሱስም ፡ ይፈርድባችኋል ፡ አለ ።
የማይጠፋ ፡ ፋና ፡ ነው ፡ በሃይማኖት ፡ የሚገኝ ፡ ፵፯፤
ሕይወትም ፡ ነው ።
ከዚህ ፡ ዘመን ፡ በኋላ ፡ ሰው ፡ ሆኖ ፡ ወደዚህ ፡ ፵፰፤
ዓለም ፡ ለመምጣቱ ፡ ሦስት ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ሦስት ፡
የቀን ፡ ሱባዔ ፡ ይደረጋል ።
በገነት ፡ ያለ ፡ ያልተተከለም ፡ ድኅነት ፡ ያለው ፡ ፵፱፤
እንጨት ፡ ነው ፡ ፍሬ ፡ የሚያወጡ ፡ እንጨቶ
ችንም ፡ ሁሉ ፡ ፍሬ ፡ እንዲያወጡ ፡ ያደርጋቸ
ዋል ፡ የደረቁትም ፡ እንጨቶች ፡ ወደሱ ፡ ይመጡ ፡
ዘንድ ፡ እንዲመጡ ፡ ያደርጋቸዋል ።
ፍሬም ፡ ያስገኙ ፡ ዘንድ ፡ ፍሬ ፡ እንዲያስገኙ ፡ ፶፤
ይለመልሙም ፡ ዘንድ ፡ እንዲለመልሙ ፡ ያደር
ጋቸዋል ፡ ፍሬያቸውም ፡ (ልጆቻቸው ፡) ከመ
ላእክት ፡ ጋር ፡ ይኖራል ፡ የእንጨቶችንም ፡
ተክል ፡ እንዲለመልሙ ፡ ያድጉም ፡ ዘንድ ፡ እን
ዲያድጉ ፡ ያደርጋቸዋል ፡ ስሩ ፡ ምድርን ፡ እን
ዳልያዘ ፡ ተክል ፡ ሥራቸው ፡ እንዳይደርቅ ፡ ለሰ
ማያዊ ፡ እግዚአብሔር ፡ ግብርን ፡ እንስጥ ፡ (ምስ
ጋናን ፡) ቀይ ፡ መልክ ፡ ያለው ፡ ቀለምም ፡ እንደ ፡
ብዝት ፡ ይነጣል ።
የጣፈጠው ፡ ውሀ ፡ መራራ ፡ ይሆናል ፡ መራራ ፶፩፤
ውም ፡ ውሀ ፡ የጣፈጠ ፡ ይሆናል ፡ በወለደው ፡
ልጁ ፡ እንደበት ፡ (ትምህርት ፡) ነገር ፡ ፍሬን ፡
ያፈሩ ፡ ዘንድ ፡ ፈጣሪ ፡ እግዚአብሔር ፡ በፍጹም ፡
ተድላ ፡ ደስታ ፡ ደሴቶችን ፡ ይመርቃቸዋል ።
እሱም ፡ ራሱ ፡ ሰው ፡ ሆኖ ፡ ወደዚህ ፡ ዓለም ፡ ፶፪፤
ይገባል ፡ እኔ ፡ ሰው ፡ ሆኜ ፡ ያየሁት ፡ ከባሕርይ ፡
አባቱም ፡ ወደዚህ ፡ ዓለም ፡ የተላከ ፡ ሰው ፡
ሁኖም ፡ ወደዚህ ፡ ዓለም ፡ የመጣ ፡ እሱ ፡ አብሯ
ቸው ፡ ይታይ ፡ ዘንድ ፡ ይገለጥላቸውም ፡ ዘንድ ፡
አሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ሐዋርያትን ፡ ለሱ ፡ አገልጋ
ዮች ፡ ሊሆኑ ፡ ይመረጣል ፡ ለማስተማር ፡ ወደ ፡
ደብረ ፡ ዘይት ፡ ይወርዳል ፡ የተራቡችንም ፡ ሰው
ነት ፡ ሁሉ ፡ ያጠግባል ።
ወደዚህ ፡ ዓለም ፡ እንዲመጣ ፡ ኤርምያስ ፡ የአ ፶፫፤
ምላክን ፡ ልጅ ፡ ነገር ፡ እንዲህ ፡ አድርጎ ፡ ተናገረ ።
ሕዝቡም ፡ ይህንን ፡ ነገር ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ ኤርም ፶፬፤
ያስ ፡ የአምላክ ፡ ልጅ ፡ አምላክን ፡ አየሁት ፡
ብሎ ፡ ስለ ፡ ተናገረው ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ተቈጡ ፡
አሁንም ፡ ተነሡ ። በኢሳይያስ ፡ እንዳደረግን ፡

በሱም ፡ እናድርግበት ፡ አሉ ። አኩሉዮቹ ፡ በደ
ንጊያ ፡ ወግረን ፡ እንግደለው ፡ እንጂ ፡ አይሆ
ንም ፡ አሉ ።
፳፬፤ አቤሜሌክና ፡ ባሮክም ፡ በዚች ፡ ሞት ፡ አትግ
ደሉት ፡ ብለው ፡ ጮሁላቸው ፡ አቤሜሌክና ፡ ባሮ
ክም ፡ ስለ ፡ ኤርምያስ ፡ አዘኑ ።
፳፭፤ ዳግመኛም ፡ ያያቸው ፡ የተሠወሩ ፡ ምሥጢሮ
ችን ፡ ይነግራቸው ፡ ዘንድ ፡ አልተዉትም ፡ ኤር
ምያስም ፡ ያየሁትን ፡ ሁሉ ፡ እስክስተምራችሁ ፡
ድረስ ፡ እኔን ፡ መግደል ፡ አይችሉምና ፡ አታል
ቅሱ ፡ አላቸው ።
፳፮፤ አሁንም ፡ እንዲት ፡ ደንጊያ ፡ አምጡልኝ ፡ አላ
ቸው ፡ እነሱም ፡ እንዲት ፡ ደንጊያ ፡ አመጡ
ለት ፡ እሱም ፡ አቁማት ፡ የዘለዓለም ፡ ብርሃን ፡
የምትሆን ፡ አንተ ፡ ይህንን ፡ ደንጊያ ፡ የሰው ፡
መልክ ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ መልክ ፡
አድርግልኝ ፡ አለ ።
፳፯፤ ያን ፡ ጊዜም ፡ ደንጊያው ፡ ኤርምያስን ፡ በመ
ልክ ፡ የሚመስለው ፡ ሆነ ፡ ኤርምያስን ፡ መሰላ
ቸው ፡ ደንጊያውን ፡ በደንጊያ ፡ ይወግሩት ፡
ጀመር ፡ ወንጀሉንም ፡ ጨረሱ ።
፳፰፤ ኤርምያስ ፡ ግን ፡ ያያቸው ፡ ምሥጢሮችን ፡
ሁሉ ፡ ለአቤሜሌክና ፡ ለባሮክ ፡ ነገራቸው ፡ ይህ
ነንም ፡ ነግሯቸው ፡ ከጨረሰ ፡ በኋላ ፡ ምግብና
ውን ፡ ይፈጽም ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ሄዶ ፡ በሕዝቡ ፡
መካከል ፡ ቆመ ።
ያንጊዜም ፡ ያ ፡ ደንጊያ ፡ እናንተ ፡ ሰነፎች ፡ የእስ ፴፤
ራኤል ፡ ልጆች ፡ ኤርምያስን ፡ አስመሰላች
ሁኝ ፡ በደንጊያ ፡ ስለምን ፡ ትወግሩኛላችሁ ፡
ኤርምያስስ ፡ እነሆ ፡ በመካከላችሁ ፡ ቁሟል ፡
ብሎ ፡ ጮኸለት ።
ኤርምያስንም ፡ ባዩት ፡ ጊዜ ፡ ብዙ ፡ ደንጊያ ፡ ፴፩፤
ይዘው ፡ ወደሱ ፡ ሮጡ ፡ እሱም ፡ ምስክርነቱን ፡
ጨረሰ ፡ እሱንም ፡ ቀበሩት ፡ ያንንም ፡ ደንጊያ ፡
አምጥተው ፡ በመቃብሩ ፡ አፍ ፡ እንደ ፡ መዝ
ጊያ ፡ አድርገው ፡ አኖሩት ።
የኤርምያስ ፡ ረዳቱ ፡ እነሆ ፡ ይህ ፡ ደንጊያ ፡ ፴፪፤
ነው ፡ ብለው ፡ በውስጡ ፡ ጻፉ ፡ የኤርምያስም ፡
የቀረች ፡ ነገሩ ፡ እነሆ ፡ በባሮክ ፡ መጽሐፍ ፡
ተጽፋለች ።
እነቃቅቶ ፡ ላስጀመረን ፡ አስጀምሮ ፡ ላስፈጸ ፴፫፤
መን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በውነት ፡ ለዘለዓለሙ ፡
ክብር ፡ ምስጋና ፡ ይግባውና ፡ ባሮክ ፡ በዚህ ፡
መጽሐፍ ፡ የተናገረው ፡ ነገር ፡ ተፈጸመ ።

# ሶ ስ ና ።

፩ በባቢሎን ፡ የሚኖር ፡ ስሙ ፡ ኢዮአቄም ፡
የሚባል ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ነበር ።
፪ ስሟ ፡ ሶስና ፡ የምትባል ፡ ሚስት ፡ አግብቶ ፡
ነበር ። ይቺውም ፡ የኬልቅዩስ ፡ ልጅ ፡ ናት ፡
እጅግ ፡ መልከ ፡ መልካም ፡ ነበረች ፡ ፈጣሪዋ ፡
እግዚአብሔርንም ፡ ትፈራው ፡ ነበር ፡ እናት ፡
አባቷም ፡ ደጋግ ፡ ሰዎች ፡ ነበሩ ። ለልጃቸውም ፡
ሙሴ ፡ የጻፋት ፡ ኦሪትን ፡ አስተምረዋት ፡ ነበር ።
፫ ባሏ ፡ ኢዮአቄም ፡ ግን ፡ እጅግ ፡ ባለጸጋ ፡ ነበር ፡
በቤቱም ፡ አጠገብ ፡ የተክል ፡ ቦታ ፡ ነበረው ፡
ከሁሉ ፡ እሱ ፡ ይከብር ፡ ነበርና ፡ አይሁድም ፡
ወደሱ ፡ ይመጡ ፡ ነበር ።
፬ ኃጢአት ፡ ከባቢሎን ፡ እንደ ፡ መጣች ፡ ሕዝ
ቡን ፡ እንጠብቃቸዋለን ፡ ከሚሉ ፡ ከግብዞች ፡
ጦገኖችም ፡ እንደ ፡ ወጣች ፡ እግዚአብሔር ፡
ስለነሱ ፡ የተናገረባቸው ፡ ግብዞች ፡ የሚሆኑ ፡
ሁለት ፡ መምህራን ፡ በዚያ ፡ ወራት ፡ ታዩ ።
፭ እነሱም ፡ በኢዮአቄም ፡ ቤት ፡ ያገለግሉ ፡ ነበር ፡
የሚፈራረዱ ፡ ሰዎችም ፡ ሁሉ ፡ ወደሱ ፡ ይመጡ ፡
ነበር ።
፮ ሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ቤታቸው ፡ ከገቡ ፡ በኋላ ፡
ቀትር ፡ በሆነ ፡ ጊዜ ፡ ሶስና ፡ ወደ ፡ ባሏ ፡ ተክል ፡
ቦታ ፡ ገብታ ፡ በዚያ ፡ ትመላለስ ፡ ነበር ።
፯ ገብታ ፡ በተመላለሰች ፡ ጊዜ ፡ እነዚያ ፡ መምህ
ራን ፡ ሁለጊዜ ፡ ያይዋት ፡ ነበር ፡ እሷንም ፡ ወደ
ዷት ።
፰ ልቡናቸውን ፡ ለወጡ ፡ ሰማይንም ፡ እንዳያዩ ፡
ዓይናቸውን ፡ ግልብጥብጥ ፡ አደረጉ ፡ (ሰማ
ያዊ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንዳያስቡ ፡) እውነ
ተኛ ፡ ሕግንም ፡ አላሰቡም ።
፱ ሁለቱም ፡ ሁሉ ፡ ወደዷት ፡ ፈቃዳቸውን ፡ መና
ገር ፡ አፍረዋልና ።
፲ እስበሳቸው ፡ በልቡናቸው ፡ ያለውን ፡ ነገር ፡
አልተናገሩም ፡ ይደርሱባት ፡ ዘንድ ፡ ይወዱ ፡
ነበር ።
፲፩ ያገኟት ፡ ዘንድ ፡ ሁለጊዜ ፡ ይጠብቋት ፡ ነበር ።
፲፪ አንዱ ፡ አንዱን ፡ የምሳ ፡ ጊዜ ፡ ነውና ፡ ወደ ፡
ቤታችን ፡ እንግባ ፡ አለው ። እየራሳቸው ፡ ተለ
ያይተው ፡ ሄዱ ።
፲፫ ተመልሰውም ፡ በኅዳና ፡ አንድነት ፡ ተገናኙ ፡
ሁለቱ ፡ ሁሉ ፡ ተያዩ ። ያንጊዜም ፡ ፈቃዳቸውን ፡
ተነጋገሩ ። ብቻ ፡ ለብቻ ፡ እሷን ፡ የሚያገኙበ
ትን ፡ ጊዜ ፡ ተቃጠሩ ።
፲፬ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ቀን ፡ ሲጠብቋት ፡ ሶስና ፡ ሁለ
ጊዜም ፡ ትገባ ፡ እንደ ፡ ነበር ፡ ከሁለቱ ፡ ደንገጡ
ሮቿ ፡ ጋራ ፡ ገባች ፡ አልቧታልና ፡ በተክል ፡
ውስጥ ፡ ትታጠብ ፡ ዘንድ ፡ ወደደች ።
፲፭ ተሠውረው ፡ ከሚጠብቋት ፡ ከሁለቱ ፡ መምህ
ራን ፡ በቀር ፡ በዚያ ፡ ማንም ፡ ማን ፡ አልነበረም ።
፲፮ ዘይት ፡ አምጥተው ፡ ያጥቧት ፡ ዘንድ ፡ ልትታ
ጠብ ፡ የተክሉንም ፡ ደጃፍ ፡ በር ፡ ይዘጉ ፡ ዘንድ ፡
ደንገጡሮቿን ፡ አዘዘቻቸው ።
፲፯ እነሱም ፡ እንዳዘዘቻቸው ፡ አደረጉ ፡ የተክሉን ፡
ደጃፍ ፡ ዘግተው ፡ ያዘዘቻቸውን ፡ ያመጡ ፡
ዘንድ ፡ በሥርጥ ፡ ኅዳና ፡ ወጡ ፡ የተሠወሩ ፡ እነ
ዚያን ፡ መምህራን ፡ ግን ፡ አላይዋቸውም ፡ ነበር ።
እነዚያ ፡ ደንገጡሮች ፡ ከወጡ ፡ በኋላ ፡ እነዚያ ፡ ፲፰
ሁለቱ ፡ መምህራን ፡ ተነሥተው ፡ ወደሷ ፡ ሮጡ ።
እነሆ ፡ የተክሉ ፡ ደጃፍ ፡ ተዘግቷል ፡ የሚያይ ፡ ፲፱
የለም ፡ እንደርስብሽ ፡ ዘንድ ፡ እንወዳለን ፡ እሺ ፡
በዪን ።
ይህ ፡ ካልሆነ ፡ ካንቺ ፡ ጋራ ፡ ሰውን ፡ እንዳገኘን ፡ ፳
ተናግረን ፡ እናጣላሻለን ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ደንገ
ጡሮችሽን ፡ ካንቺ ፡ አስወጥተሽ ፡ ሰደድሽ ፡
አሏት ።
ሶስናም ፡ አለቀሰች ፡ በሁሉም ፡ ፈጽሚ ፡ ተጨ ፳፩
ነቀሁ ፡ ባደርገውም ፡ እሞታለሁ ፡ ባላደርገ
ውም ፡ አልድንም ፡ ከእጃቸው ፡ ማምለጥንም ፡
አልችልም ።
እግዚአብሔርን ፡ ከምበድል ፡ ኃጢአትስ ፡ ፳፪
ልሠራ ፡ በእጃቸው ፡ መውደቅ ፡ ይሻለኛል ፡
አለች ።
ሶስና ፡ ቃሏን ፡ አሰምታ ፡ ጮኸች ፡ እነዚያም ፡ ፳፫
መምህራን ፡ ከሷ ፡ ጋራ ፡ ጮሁ ።
አንዱ ፡ ሮጦ ፡ ሄዶ ፡ የተክሉን ፡ ደጃፍ ፡ ከፈተ ። ፳፬
በቤቷም ፡ ያሉ ፡ ሰዎች ፡ በተክል ፡ መካከል ፡ ፳፭
ጩኸትን ፡ ሰምተው ፡ ወጡ ፡ ምንም ፡ እንደ ፡
ሆነች ፡ ያዩ ፡ ዘንድ ፡ በሥርጥ ፡ ኅዳናም ፡ ሮጡ ።
እነዚህ ፡ ሁለቱ ፡ መምህራን ፡ ይህንን ፡ ነገር ፡ ፳፮
በተናገሩ ፡ ጊዜ ፡ በሶስና ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡
ፈጽሞ ፡ ተሰምቶ ፡ አያውቅም ፡ ነበርና ፡ ዘመዶ
ቿና ፡ ባሮቿ ፡ እጅግ ፡ አፈሩ ።
በማግሥቱ ፡ ሕዝቡ ፡ በባሏ ፡ በኢዮአቄም ፡ ፳፯
ዘንድ ፡ በተሰበሰቡ ፡ ጊዜ ፡ እነዚያ ፡ ሁለቱ ፡ መም
ህራን ፡ ሶስናን ፡ ይገድሏት ፡ ዘንድ ፡ ከመፀኛ ፡
ልቡናቸው ፡ ጋራ ፡ መጡ ፡ በሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡
ፊት ።
ያመጧት ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ኢዮአቄም ፡ ሚስት ፡ ፳፰
ወደ ፡ ሶስና ፡ ላኩ ፡ አሉ ፡ ወደሷም ፡ ላኩባት ።
እሷም ፡ ከናት ፡ ከባቷ ፡ ከወገኖቿ ፡ ከዘመዶ ፳፱
ቿም ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ መጣች ።
ሶስና ፡ ግን ፡ እጅግ ፡ ደመ ፡ ግቡ ፡ ነበረች ፡ መል ፴
ኳም ፡ ያማረ ፡ ነበር ።
ዓመፀኞች ፡ የሚሆኑ ፡ እነዚያም ፡ ሁለቱ ፡ መም ፴፩
ህራን ፡ መልኳን ፡ ለመጥገብ ፡ ከንብንቧን ፡ ይገ
ልጧት ፡ ዘንድ ፡ አዘዙ ፡ ከንብንቧንም ፡ ገለ
ጧት ።
አባቷ ፡ እናቷ ፡ ቤተ ፡ ሰቦቿ ፡ የሚያውቋትም ፡ ፴፪
ሁሉ ፡ አለቀሱላት ።
እነዚያም ፡ ሁለቱ ፡ መምህራን ፡ በሕዝቡ ፡ መካ ፴፫
ከል ፡ ተነሥተው ፡ እጆቻቸውን ፡ በራሷ ፡ ላይ ፡
አኖሩ ።
እሷ ፡ ግን ፡ ልቡናዋ ፡ በእግዚአብሔር ፡ አምኗ ፴፬
ልና ፡ እያለቀሰች ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ አየች ።
እነዚያም ፡ መምህራን ፡ ብቻችንን ፡ በተክል ፡ ፴፭
ውስጥ ፡ ስንመላለስ ፡ እሷ ፡ ከሁለቱ ፡ ደንገጡ
ሮቿ ፡ ጋራ ፡ ገባች ፡ ደንገጡሮቿን ፡ ልካቸዋለ
ችና ፡ የተክሉን ፡ ደጃፍ ፡ ዘግተው ፡ ሄዱ ፡ ደን
ገጡሮቿን ፡ ከላከቻቸውም ፡ በኋላ ።

፴፮ አንድ ፡ ጕልማሳ ፡ ከተሠወረበት ፡ መጥቶ ፡ ደረ
ሰባት ።
፴፯ እኛ ፡ ግን ፡ በዚያ ፡ ተክል ፡ ዳርቻ ፡ ሆነን ፡ ኃጢ
አታቸውን ፡ አየን ፡ ወደነሱቸውም ፡ ሮጠን ፡
ሄድን ፡ አንድነት ፡ ተኝተው ፡ አገኘናቸው ።
፴፰ እኛ ፡ ግን ፡ እሱን ፡ መያዝ ፡ ተሳነን ፡ እሱ ፡ በር
ትቶብናልና ፡ አመለጠን ፡ የተከሉን ፡ ደጃፍ ፡
ከፍቶ ፡ ወጣ ።
፴፱ እሷን ፡ ግን ፡ ያዝናት ፡ ሰውየው ፡ ማን ፡ እንደ ፡
ሆነ ፡ ጠየቅናት ፡ ነገር ፡ ግን ፡ አልነገረችንም ፡
አሉ ።
፵ የሕዝቡ ፡ መምህራን ፡ ናቸውና ፡ ገዢዎች ፡ ናቸ
ውና ፡ በደባባይ ፡ የተሰበሰቡ ፡ ሰዎች ፡ ነገራቸ
ውን ፡ አመኗቸው ፡ ትሞት ፡ ዘንድ ፡ ፈረዱባት ።
፵፩ ሶስናም ፡ ቃሏን ፡ አሰምታ ፡ ጮኸች ፡ ዘለዓለም ፡
ጸንተህ ፡ የምትኖር ፡ የተሠወረውን ፡ የምታ
ውቅ ፡ የሚደረገውን ፡ ሁሉ ፡ ሳይደረግ ፡ የምታ
ውቅ ፡ ፈጣሪ ፡ ሆይ ።
፵፪ በሐሰት ፡ እንደ ፡ ጣሉኝ ፡ አንተ ፡ ታውቃለህ ፡
እነዚህ ፡ መምህራን ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡ ባደረጉብኝ ፡
ገንዘብ ፡ የሠራሁት ፡ ኃጢአት ፡ ሳይኖር ፡ እነሆ ፡
እሞታለሁ ፡ አለች ።
፵፫ እግዚአብሔርም ፡ ቃሏን ፡ ሰማት ።
፵፬ ይገድሏት ፡ ዘንድ ፡ ሲወስዷት ፡ እግዚአብሔር ፡
ስሙ ፡ ዳንኤል ፡ የሚባል ፡ የልጅ ፡ ልቡናን ፡
አነሣሣ ።
፵፭ እኔ ፡ ከዚች ፡ ሴት ፡ ደም ፡ ንጹሕ ፡ ነኝ ፡ ብሎ ፡
ቃሉን ፡ አሰምቶ ፡ ተናገረ ።
፵፮ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ወደሱ ፡ ተመለሱ ፡ አንተ ፡
የምትናገረው ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ ምንድነው ፡ አሉ ።
፵፯ ዳንኤልም ፡ በመካከላቸው ፡ ቆሞ ፡ አላዋቆች ፡
የምትሆኑ ፡ እናንተ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡
ሳትመረምሩ ፡ ነገሩን ፡ ሳትረዱ ፡ በእስራኤል ፡
ልጅ ፡ እንዲህ ፡ አደረጋችሁ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡
ፍርድን ፡ ትፈርዱላችሁን ።
፵፰ እነዚህ ፡ መምህራን ፡ በሐሰት ፡ አጣልተዋታ
ልና ፡ ወደ ፡ አደባባይ ፡ ተመለሱ ፡ አላቸው ።
፵፱ ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ እየሮጡ ፡ ወደ ፡ አደባባይ ፡
ተመለሱ ፡ አለቆችም ፡ ዳንኤልን ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ አንተን ፡ አልቆሃልና ፡ በመካከላችን ፡
ተቀምጠህ ፡ ንገረን ፡ አሉት ።
፶ ዳንኤልም ፡ እየራሳቸው ፡ አራርቃችሁ ፡ አቁ
ሟቸው ፡ እኔም ፡ ልመርምራቸው ፡ አላቸው ።
፶፩ አንዱንም ፡ አንዱንም ፡ አራርቀው ፡ አቆሟ
ቸው ፡ ከነሱቸውም ፡ አንዱን ፡ ጠርቶ ፡ ዘመ
ንህ ፡ አርጅቷል ፡ እነዚህም ፡ ክፉዎች ፡ ናቸው ፡
ቀድሞ ፡ የሠራሃቸው ፡ ኃጢአቶችህ ፡ ፍዳውን ፡
ይዘው ፡ ደረሱብህ ።
፶፪ የሐሰት ፡ ፍርድን ፡ ፈርደሃልና ፡ ይሞት ፡ በቃ
ውን ፡ ይድን ፡ በቃ ፡ ብለህ ፡ ፈርደሃልና ፡ ጻድ
ቁን ፡ ንጹሑን ፡ አትግደል ፡ ብሎ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ የከለከለውን ፡ ይድን ፡ በቃውን ፡ ይሞት ፡
በቃ ፡ ብለህ ፡ ፈርደሃልና ፡ ኃጢአቶችህ ፡ ፍዳ
ውን ፡ ይዘው ፡ ደረሱብህ ።

አሁንም ፡ ይቺን ፡ ሴት ፡ ካየሃት ፡ ሁለቱን ፡ ሁሉ ፡ ፶፫
በምን ፡ እንጨት ፡ ስር ፡ ሲነጋገሩ ፡ አየህ ፡ ንገ
ረኝ ፡ አለው ፡ በኮክ ፡ ስር ፡ ሲነጋገሩ ፡ አየኋቸው ፡
አለ ።
ዳንኤልም ፡ በውነት ፡ ሐሰትን ፡ ተናገርህ ፡ የደ ፶፬
ምህ ፡ ፍዳ ፡ በራስህ ፡ ነው ፡ ከመካከልህ ፡ ይሰነ
ጥቅህ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ የላከው ፡ መል
አክ ፡ እነሆ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ታዝዞ ፡ አለው ።
ያን ፡ መርምሮ ፡ አልፍ ፡ አደረገው ፡ ሁለተኛ ፶፭
ውን ፡ ያመጡት ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፡ አመጡት ፡
አንተ ፡ የይሁዳ ፡ ዘር ፡ ያይደለህ ፡ የከነዓን ፡ ዘር ፡
ነህ ፡ መልክ ፡ አሳተህን ፡ ክፉ ፡ ፈቃድስ ፡ ልቡና
ህን ፡ ግልብጥብጥ ፡ አደረገችህን ።
እሷ ፡ እናንተን ፡ መከራከር ፡ አልቻለችምና ፡ ፶፮
የይሁዳ ፡ ልጅ ፡ እናንተን ፡ ፈርታለችና ፡ በደላች
ሁንም ፡ ታግሣለችና ፡ እናንተ ፡ ግን ፡ በድላች
ኋታልና ፡ የእስራኤልን ፡ ልጅ ፡ እንዲህ ፡ ታደ
ርጓታላችሁን ።
አሁንም ፡ ሁለቱ ፡ ሲነጋገሩ ፡ ያየህበት ፡ እንጨት ፡ ፶፯
ምንድነው ፡ ነገረኝ ፡ አለው ፡ ሮማን ፡ በሚባል ፡
እንጨት ፡ ስር ፡ አየኋት ፡ አለው ።
ዳንኤልም ፡ አንተም ፡ በውነት ፡ ሐሰትን ፡ ተና ፶፰
ገርህ ፡ የደምህም ፡ ፍዳ ፡ በራስህ ፡ ነው ፡ ሁለታ
ችሁንም ፡ ሊያጠፋችሁ ፡ ከእኩሌታ ፡ ወገብህ ፡
ያሰነጥቅህ ፡ ዘንድ ፡ እነሆ ፡ እግዚአብሔር ፡ የላ
ከው ፡ መልአክ ፡ ይጠብቅሃል ፡ አለው ።
ሕዝቡም ፡ ሁሉ ፡ ቃላቸውን ፡ አሰምተው ፡ ፶፱
ጮሁ ፡ ያመነችበት ፡ ሶስና ፡ ያዳናት ፡ እግዚአ
ብሔርንም ፡ አመሰገኑት ።
ከቃላቸው ፡ የተነሣ ፡ ዳንኤል ፡ ነቅሾቸዋልና ፡ ፷
ምስክርነታቸውንም ፡ ሐሰት ፡ አድርጎባቸዋ
ልና ፡ በነዚያ ፡ በሁለቱም ፡ መምራህን ፡ ላይ ፡
በጠላትነት ፡ ተነሡባቸው ፡ በባልንጀራቸው ፡
ክፉ ፡ ሥራን ፡ እንደ ፡ ሠሩ ፡ በነሳቸውም ፡
በሙሴ ፡ ሥርዓት ፡ ክፉ ፡ ሥራን ፡ ሠሩባቸው ።
በዚያችም ፡ ቀን ፡ ንጹሕ ፡ ደምን ፡ አዳኑ ። ፷፩
በሷ ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ አልተገኘምና ፡ ስለ ፡ ልጃ ፷፪
ቸው ፡ ስለ ፡ ሶስና ፡ ሚስቱና ፡ ኬልቅዩ ፡ ከዘመ
ዶቿ ፡ ሁሉና ፡ ከባሏ ፡ ከኢዮአቄም ፡ ጋራ ፡ እግ
ዚአብሔርን ፡ አመሰገኑት ።
ዳንኤልም ፡ ከዚያች ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ጊዜ ፡ ፷፫
ሞቱ ፡ ድረስ ፡ በሕዝቡና ፡ በእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ገናና ፡ ሆነ ።

# መ ጽ ሐ ፈ ፡ ባ ሮ ክ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩፤ የኬልቅዩ ፡ ልጅ ፡ ሴዴቅያስ ፡ የሴዴቅዩ ፡ ልጅ ፡
የማሴው ፡ ልጅ ፡ ኔርዩ ፡ የኔርዩ ፡ ልጅ ፡ ባሮክ ፡
ወደ ፡ ባቢሎን ፡ የጻፈው ፡ መጻፍ ፡ ነገር ፡ ይህ ፡
ነው ።
፪፤ በምስተኛው ፡ ዓመት ፡ ወሩ ፡ በባተ ፡ በስባተ
ኛው ፡ ቀን ፡ የፋርስ ፡ ሰዎች ፡ ኢየሩሳሌምን ፡
በጠፉት ፡ ጊዜ ፡ በእሳትም ፡ ባቃጠሏት ፡ ጊዜ ፡
የጻፈው ፡ ነገር ፡ ይህ ፡ ነው ።
፫፤ ከይሁዳ ፡ ንጉሥ ፡ ከኢዮአቄም ፡ ልጅ ፡ ከኢኮ
ንያን ፡ የተጻፈውን ፡ ከሕዝቡም ፡ ዘንድ ፡ ወደሱ ፡
የመጣውን ።
፬፤ የባቢሎን ፡ ሰዎች ፡ የእግዚአብሔር ፡ ማ^ሬያ ፡
ንዋየ ፡ ቅድሳቱን ፡ ከቤተ ፡ መቅደስ ፡ በወሰዱ ፡
ጊዜ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ወዳሉ ፡ ካህናት ፡ የላከው
ንም ፡ ይህንን ፡ መጽሐፍ ፡ ባሮክ ፡ አነበበ ።
፭፤ ናቡከደነፆር ፡ ኢኮንያንን ፡ ከማረከው ፡ በኋላ ፡
የኢየሩሳሌምንም ፡ ወገኖች ፡ ከማረካቸው ፡
በኋላ ፡ ወደ ፡ ባቢሎንም ፡ ከወሰዳቸው ፡ በኋላ ፡
ሴዴቅያስ ፡ የብሩን ፡ ዕቃ ፡ አሠርቶ ፡ ከወርቁ ፡
ጋራ ፡ ሰደደላቸው ።
፮፤ ዘመናቸው ፡ ጠፈር ፡ በአድማስ ፡ ጸንቶ ፡ የኖ
ረውን ፡ ያህል ፡ ጸንቶ ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ባቢ
ሎን ፡ ንጉሥ ፡ ስለ ፡ ናቡከደነፆር ፡ ድኅነት ፡
ስለ ፡ ልጁ ፡ ስለ ፡ ብልጣሰርም ፡ ድኅነት ፡ ለምኑ ፡
አለ ።
፯፤ ፈጣሪያችን ፡ እግዚአብሔርን ፡ በድለናልና ፡
ለኛም ፡ ወደ ፡ ፈጣሪያችን ፡ ወደ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ለምኑልን ፡ አለ ።
፰፤ ካህናቱ ፡ ቀድሞ ፡ ደግሞ ፡ ሕግን ፡ በበዓል ፡ ቀን ፡
ያነቢት ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ ይቺንም ፡ መጽሐፍ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ በቤተ ፡ መቅደስ ፡
አንብቧት ፡ አለ ።
፱፤ የፈጣሪያችን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቸርነት ፡ ተና
ገሩ ፡ የኢየሩሳሌምን ፡ የይሁዳን ፡ ሰዎች ፡ የኛን ፡
ፊት ፡ ኃፍረት ፡ ሸፈነን ። የመሳፍንቱንና ፡ የነገ
ሥታቱን ፡ ፊት ፡ የመምህራኑንና ፡ የካህናቱ
ንም ፡ ፊት ፡ ኃፍረት ፡ ሸፈነው ።
፲፤ የፈጣሪያችን ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ቃል ፡ አል
ሰማንም ፡ በሠራልን ፡ በፈጣሪያችን ፡ በእግዚአ
ብሔርም ፡ ትእዛዝ ፡ ጸንተን ፡ አልኖርንም ።
፲፩፤ አባቶቻችንን ፡ ከግብጽ ፡ አገር ፡ ካወጣቸው ፡
ጀምሮ ፡ እስከዚች ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ፈጣሪያችን ፡
እግዚአብሔርን ፡ መነጀልነው ።
፲፪፤ ሄደን ፡ ለአሕዛብ ፡ ጣዖቶች ፡ ተገዝተናልና ፡
በሙሴም ፡ አሪት ፡ የተጻፈው ፡ መከራ ፡ ደርሶብ
ናልና ፡ ይህ ፡ ጽኑ ፡ እርግማን ፡ አገኘን ፡ አለ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

በዚያ ፡ ወራት ፡ ሰው ፡ የሴቶች ፡ ልጆቹንና ፩፤
የወንዶች ፡ ልጆቹን ፡ ሥጋ ፡ በላ ።
እግዚአብሔርም ፡ በዙሪያችን ፡ ወዳሉ ፡ አሕ ፪፤
ዛብ ፡ በተነን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አልተገዛንም ፡
የልቡናችንንም ፡ ክፋት ፡ አልተውንም ።
አሁንም ፡ በጽኑ ፡ ኃይል ፡ በጽኑ ፡ ሥልጣንም ፡ ፫፤
ከግብጽ ፡ አገር ፡ ወገኖችህን ፡ ያወጣህ ፡ የእስራ
ኤል ፡ ፈጣሪ ፡ እግዚአብሔር ፡ በአሕዛብ ፡ ዘንድ ፡
ጥቂት ፡ ቀርተናልና ።
ቍጣህን ፡ ከኛ ፡ መልስ ፡ ፈጣሪያችን ፡ አንተ ፡ ፬፤
እግዚአብሔር ፡ ነህና ፡ ልመናችንን ፡ ሰምተህ ፡
አድነን ።
አቤቱ ፡ በመመስገኛህ ፡ ቦታ ፡ በጽርሐ ፡ አር ፭፤
ያም ፡ ሁነህ ፡ እኛን ፡ በዓይነ ፡ ምሕረት ፡ ተመ
ልከት ።
እግዚአብሔር ፡ የዳነች ፡ ሰውነት ፡ ተርበም ፡ ፮፤
የጠገበች ፡ ሰውነት ፡ ታመሰግንሃለች ፡ እንጂ ፡
በመቃብር ፡ ያሉ ፡ ሥጋት ፡ የሚያመሰግኑህ ፡
አይደሉም ።
እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡ የምነግራችሁን ፡ ፯፤
በጆሮዎቻችሁ ፡ ሰምታችሁ ፡ ለባቢሎን ፡ ንጉሥ ፡
ተገዙ ፡ ላባቶቻችሁ ፡ በሰጠኋቸው ፡ አገር ፡ ትኖ
ራላችሁ ።
የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ስትሰሙ ፡ ለባቢሎ ፰፤
ንም ፡ ንጉሥ ፡ ባትገዙ ፡ ግን ።
ከይሁዳ ፡ አገሮች ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ አደባባይ ፡ ፱፤
የፍጹም ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ቃል ፡ የሴት ፡ ሙሽ
ራን ፡ የወንድ ፡ ሙሽራ ፡ ቃል ፡ ይጠፋል ፡ አገ
ሩም ፡ ሁሉ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ይሆናል ፡ አልኸን ።
ቃልህን ፡ አልሰማንም ፡ ለባቢሎንም ፡ ንጉሥ ፡ ፲፤
አልተገዛንም ፡ የነገሥታቱን ፡ አጥንቶች ፡ ያባ
ቶቻችንንም ፡ አጥንቶች ፡ ከቦታቸው ፡ ያወጣሉ ፡
ብለህ ፡ በባልጋዮችህ ፡ በነቢያት ፡ ቃል ፡ የተና
ገርከው ፡ ደረሰብን ፡ አሉ ።
እነሆ ፡ በቀን ፡ ሐሩር ፡ በሌሊትም ፡ ቍር ፡ ጣሏ ፲፩፤
ቸው ፡ ተማርከን ፡ ሔደን ፡ በጦርና ፡ በቀጠና ፡
ክፉ ፡ አሟሟት ፡ ሞትን ።
እነዚያ ፡ ወገኖች ፡ ክፋደ ፡ ልቡናቸውን ፡ ያጸኑ ፡ ፲፪፤
ናቸውና ፡ እንዳይሰሙኝ ፡ አወቅኋቸው ።
ፈጣሪያቸው ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ፲፫፤
ያውቃሉ ፡ የሚያውቁበት ፡ ልቡናን ፡ የሚሰ
ሙበት ፡ ጆሮን ፡ እሰጣቸዋለሁ ።
በስማረኳቸው ፡ አገር ፡ ያመሰግኑኛል ፡ ስሜ ፲፬፤
ንም ፡ ያስባሉ ።
ክፉ ፡ ሥራቸውንም ፡ ይተዋሉ ፡ በእግዚአብ ፲፭፤
ሔር ፡ ፊት ፡ የበደሉ ፡ ያባቶቻቸውንም ፡ ሥራ ፡
አያስቡም ።

፲፯ ላባቶቻቸው ፡ ለይስሐቅና ፡ ለአብርሃም ፡ ለያዕ
ቆብ ፡ ወደ ፡ ማልሁላቸው ፡ አገር ፡ እመልሳቸዋ
ለሁ ፡ እነሱ ፡ ይገዙታል ፡ እኔም ፡ አበዛቸዋ
ለሁ ፡ እነሱም ፡ አያንሱም ።
፲፰ ፈጣሪያቸው ፡ እሆናቸው ፡ ዘንድ ፡ የዘለዓለም ፡
ሥርዓትን ፡ እሠራላቸዋለሁ ፡ እነሱም ፡ ወገኖ
ቼን ፡ ይሆኑኛል ፡ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ከሰጠኋቸው ፡
አገራቸው ፡ ወገኖቼ ፡ እስራኤልን ፡ አላወጣቸ
ውም ፡ አለ ።

ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ ነግሠህ ፡ የምትኖር ፡ የእስራኤል ፡ ፈጣሪ ፡
አቤቱ ፡ ያዘነችና ፡ የተራበች ፡ ሰውነት ፡ ወዳ
ንተ ፡ ጮኸች ።
፪ አቤቱ ፡ ልመናዬን ፡ ሰምተህ ፡ ይቅር ፡ በላት ፡
በፊትህ ፡ በድለናልና ።
፫ አንተም ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ትኖራለህና ፡ እኛ ፡ ግን ፡
ለዘለዓለሙ ፡ እንጠፋለንና ።
፬ ለሁሉ ፡ የምትነግሥ ፡ የእስራኤል ፡ ፈጣሪ ፡
አቤቱ ፡ ምውታን ፡ ልብ ፡ የሚሆኑ ፡ የእስራኤ
ልን ፡ ጸሎት ፡ በፊትህም ፡ የበደሉ ፡ ቃልህ
ንም ፡ ያልሰሙ ፡ የልጆችን ፡ ልመና ፡ ስማ ።
፭ ክፉ ፡ ነገርን ፡ የተከተልን ፡ ያባቶቻችንንም ፡
ኃጢአት ፡ ያላሰብን ፡ የኛንም ፡ ልመና ፡ ስማ ፡
በዚህም ፡ ወራት ፡ ስምህንና ፡ ሥልጣንህን ፡
አስብ ።
፮ እግዚአብሔር ፡ አንተ ፡ ፈጣሪያችን ፡ ነህና ፡
አቤቱ ፡ እኛም ፡ እናመሰግንሃለንና ።
፯ ስምህን ፡ እንጠራ ፡ ዘንድ ፡ ማርከው ፡ በወሰዱ
ንም ፡ ሰዎች ፡ ዘንድ ፡ አንተን ፡ እናመሰግንህ ፡
ዘንድ ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ መፈራትህን ፡ በልቡና
ችን ፡ አሳደርህ ።
፰ እስራኤል ፡ ድኅነት ፡ ያለበትን ፡ ትእዛዝ ፡ የጥ
በብንም ፡ ምክር ፡ ስማ ።
፱ እስራኤል ፡ ምንድነው ፡ በጠላትስ ፡ አገር ፡
ለምን ፡ ኖረ ።
፲ በባዕድ ፡ አገርስ ፡ ለምን ፡ ጠፋ ፡ እንደ ፡ እሬ
ሳስ ፡ ለምን ፡ ረከሰ ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ እንደ ፡
ወረዱ ፡ ሰዎችስ ፡ ለምን ፡ ተቈጠረ ።
፲፩ የሕይወት ፡ መገኛ ፡ ሕጉንስ ፡ ለምን ፡ ተወ ።
፲፪ በእግዚአብሔርስ ፡ ሕግ ፡ ጸንተህ ፡ ብትኖር ፡
ለዘለዓለም ፡ በተድላ ፡ በደስታ ፡ በኖርክ ፡ ነበር ።
፲፫ ተማር ፡ ጥበብ ፡ ከየት ፡ ተገኘ ፡ ኃይልስ ፡ ከየት ፡
ተገኘ ፡ እውቀትና ፡ ምክርስ ፡ ከየት ፡ ተገኘ ፡
ብዙ ፡ ዘመን ፡ በሕይወት ፡ መኖርስ ፡ ከየት ፡
ተገኘ ፡ የዓይኖች ፡ ብርሃንስ ፡ ከየት ፡ ተገኙ ።
፲፬ የጥበብንስ ፡ አገሯን ፡ ማን ፡ አገኘው ፡ ምሥጢ
ሮቿን ፡ ማን ፡ መረመረው ።
፲፭ የምድረ ፡ በዳ ፡ አውሬዎችን ፡ የገዟቸው ፡
፲፮ በሰማይ ፡ የሚበሩ ፡ አዕዋፍንም ፡ የተጫወቱ
ባቸው ፡ የአሕዛብ ፡ አለቆችስ ፡ ወዴት ፡ ናቸው ።
፲፯ እነሱስ ፡ ሙተው ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ወረዱ ፡
ስለነሱም ፡ ፈንታ ፡ ሌሎች ፡ ተተኩ ።
ትሩፋን ፡ ተድላ ፡ ደስታን ፡ አዩ ፡ በገራቸውም ፡ ፲፰
ኖሩ ፡ የጥበብን ፡ ሥራ ፡ ግን ፡ አላወቋም ። (ዘጠ
ኙን ፡)
ፍለጋውንም ፡ (ኢታምልክ ፡) አላገኙትም ፡ ፲፱
ልጆቻቸውም ፡ አልተቀበሉትም ፡ ከሕጋቸ
ውም ፡ ራቁ ።
የከነዓን ፡ ሰዎች ፡ ይህነን ፡ አልሰሙም ፡ የቴም ፳
ናም ፡ ሰዎች ፡ አላዩም ።
በእስራኤል ፡ አገር ፡ ጥበብን ፡ የሚፈልጓት ፡ ፳፩
የአርበኞችም ፡ ልጆች ፡ ይህነን ፡ አላወቁም ።
የእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ፳፪
እንዴት ፡ ሰፊ ፡ ታላቅ ፡ ነበር ፡ በሱም ፡ የሚገ
ኘው ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ፍጻሜ ፡ የለውም ፡ ነበር ፡
ስፍር ፡ ቍጥርም ፡ የለውም ፡ ነበር ።
ወደ ፡ ሰማይ ፡ ወጥቶ ፡ ሕግን ፡ የተቀበላት ፡ ከደ ፳፫
መናትስ ፡ ያወረዳት ፡ ማነው ።
ባሕሩን ፡ ተሻግሮ ፡ ሄዶ ፡ ያገኛት ፡ በቀይስ ፡ ፳፬
ወርቅ ፡ ገዝቶ ፡ ያመጣት ፡ ማነው ።
ጐዳናዋን ፡ የሚያውቅ ፡ ፍለጋዋንም ፡ የሚያ ፳፭
ስብ ፡ ማነው ።
ሁሉን ፡ የሚያውቅ ፡ ጌታ ፡ ያውቃታል ፡ ሰማይ ፳፮
ንና ፡ ምድርን ፡ የፈጠረ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእ
ውቀቱ ፡ አገኛት ።
ብርሃኑን ፡ ያመጣላቸዋል ፡ በብርሃኑም ፡ ጸን ፳፯
ተው ፡ ይኖራሉ ።
ከዋክብትም ፡ በጊዜያቸው ፡ ያበራሉ ፡ በዚ ፳፰
ሁም ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
ይጠራቸዋል ፡ እሱን ፡ የሚመስል ፡ ሌላ ፡ የለ ፳፱
ምና ፡ ፈጣሪያችን ፡ ወዳንተ ፡ መጣን ፡ ይላሉ ።
የጥበብን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ እሱ ፡ አገኛት ፡ ለባለ ፴
ሟሉ ፡ ለያዕቆብ ፡ ለወዳጁም ፡ ለእስራኤል ፡
ሰጠው ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በምድር ፡ ተገለጠ ፡ እንደ ፡ ፴፩
ሰውም ፡ ሆነ ።

ምዕራፍ ፡ ፬ ።

የእግዚአብሔር ፡ ትእዛዝ ፡ የተጻፈበት ፡ መጽ ፩
ሐፍ ፡ ይህ ፡ ነው ፡ በሱም ፡ ጸንተው ፡ ለዘለዓ
ለም ፡ ይኖራሉ ፡ እሷንም ፡ የሚጠብቋት ፡ ሰዎች ፡
ለዘለዓለም ፡ ይኖራሉ ፡ የሚተዉዋት ፡ ሰዎች ፡
ግን ፡ ይሞታሉ ።
ያዕቆብ ፡ ተመልሰህ ፡ ሕግን ፡ ያዝ ፡ በሥርዓቷም ፡ ፪
ጸንተህ ፡ ኑር ።
ከሌላ ፡ ወገን ፡ የሚሻል ፡ ክብርህንም ፡ ለሌላ ፡ ፫
አትስጥ ።
የፈጣሪያችን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቸርነቱ ፡ በኛ ፡ ፬
ታውቋልና ፡ እስራኤል ፡ እኛ ፡ የተደነቅን ፡ ነን ።
ወገኖቼ ፡ እመኑ ፡ እስራኤልም ፡ ቸርነቱን ፡ አስቡ ። ፭
ለጥፋት ፡ ያይደለ ፡ ወገኖቼ ፡ ልትሆኑኝ ፡ ተወ ፮
ጀጅኋችሁ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አበሳጭታችሁ
ታልና ።
ፈጣሪያችሁን ፡ አውከቻችሁታልና ፡ ለእግዚአብ ፯
ሔር ፡ ያይደለ ፡ ለአጋንንት ፡ መሥዋዕት ፡ ሠው
ታችኋልና ።

፳፯ ለዘለዓለም ፡ ያሳደጋችሁ ፡ ፈጣሪያችሁንም ፡
ዘንግታችሁታልና ፡ የመጣበችሁን ፡ የእግዚአ
ብሔርን ፡ መቅሠፍት ።
፳፰ ባየች ፡ ጊዜ ፡ ሞግዚታችሁ ፡ ኢየሩሳሌምን ፡
አሳዝናችኋታልና ፡ ነገር ፡ ግን ፡ በጠላቶቻችሁ ፡
እጅ ፡ ወደቃችሁ ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ የተሰደዳ
ችሁ ፡ ሰዎች ፡ ስሙ ።
፳፱ የወንዶች ፡ ልጆቼንና ፡ የሴቶች ፡ ልጆቼን ፡
መማረክ ፡ ባየሁ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ታላቅ ፡
ልቅሶን ፡ አመጣብኝ ።
፴ እግዚአብሔር ፡ ስም ፡ ያወጣልሽ ፡ ኢየሩሳሌም ፡
እምነሽ ፡ ደስ ፡ ይበልሽ ።
፴፩ መከራ ፡ ያጸኑብሽ ፡ በንቺ ፡ ጥፋት ፡ ደስ ፡ ያላ
ቸው ፡ ሰዎች ፡ ይጐሰቍላሉ ።
፴፪ ልጆችሽን ፡ የገዙ ፡ ልጆችሽንም ፡ ማርከው ፡
የወሰዱ ፡ አገሮች ፡ ይጠፋሉ ።
፴፮ ኢየሩሳሌም ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ እዩ ፡ ከፈጣ
ሪሽ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የመጣልሽ ፡
ተድላ ፡ ደስታውንም ፡ እስተውዩ ።
፴፯ እነሆ ፡ ልጆችሽ ፡ ከተማረኩበት ፡ አገር ፡ መጡ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ከምሥራቅ ፡ እስከ ፡ ምዕ
ራብ ፡ የሰደድሻቸው ፡ ወገኖችሽም ፡ ተሰበሰቡ ፡
በእግዚአብሔርም ፡ ተአምራት ፡ ደስ ፡ ይላቸ
ዋል ።

ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ ኢየሩሳሌም ፡ የመከራሽንና ፡ የኃዘንሽን ፡
ልብስ ፡ ካንቺ ፡ አርቂው ፡ ለዘለዓለም ፡ ከእግዚ
አብሔር ፡ ዘንድ ፡ የታዘዘልሽ ፡ የምትከብሪበ
ትን ፡ ጌጥ ፡ ልበሽ ።
፪ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የተገኘ ፡ የክብር ፡
መጐናጸፊያሽን ፡ ተጐናጸፊ ፡ በእግዚአብሔ
ርም ፡ ጌትነት ፡ ዘውድሽን ፡ በራስሽ ፡ ላይ ፡ ድፊ ፡
አላት ።
፫ እግዚአብሔር ፡ ከሰማይ ፡ በታች ፡ ላሉ ፡ ሁሉ ፡
ብርሃንሽን ፡ ገልጧልና ።
፬ ስምሽም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ለዘለዓለም ፡
ይጠራልና ፡ ፍቅርና ፡ ቸርነት ፡ እግዚአብሔርን ፡
መፍራትና ፡ ጌትነት ፡ ይደረግልሻልና ፡ ዘውድ
ሽን ፡ ድፊ ።
፭ ኢየሩሳሌም ፡ ተነሥተሽ ፡ በላይኛው ፡ በታ ፡
ቁሚ ፡ ወደ ፡ ምሥራቅም ፡ እዩ ፡ ከፀሐይ ፡
መግቢያ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ምሥራቅ ፡ ድረስ ፡
በእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ልጆችሽ ፡ እንደተሰበ
ሰቡ ፡ እስተውዩ ፡ እግዚአብሔርንም ፡ በመፍ
ራት ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
፮ ካንቺ ፡ ተማርከው ፡ ሔዱ ፡ ጠላቶቻቸውም ፡
በእግራቸው ፡ ወሰዷቸው ፡ እግዚአብሔር ፡
ግን ፡ በክብር ፡ ተሸክመው ፡ ከንጉሡ ፡ ዙፋን ፡
ጋራ ፡ ወዳንቺ ፡ እንዲያመጧቸው ፡ ያደርጋል ።
እግዚአብሔርም ፡ረጃጅሞች ፡ ተራሮች ፡ ሁሉ ፡ ፯
ይዋረዱ ፡ ዘንድ ፡ ጉድጓዳውም ፡ ሁሉ ፡ ይመላ ፡
ዘንድ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ጌትነት ፡ እስራኤል ፡
ጥርጊያውን ፡ ጐዳና ፡ እንዲሔድ ፡ ምድሩም ፡
ይትክከል ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ።
እስራኤልን ፡ በእስራኤል ፡ ፈጣሪ ፡ በእግዚአብ ፰
ሔር ፡ ትእዛዝ ፡ በተድላ ፡ በደስታ ፡ በጌትነቱም ፡
ብርሃን ፡ በቸርነቱና ፡ በይቅርታውም ፡ ዛፉ ፡
ሁሉ ፡ በጎ ፡ መዓዛ ፡ ያለው ፡ እንጨቱም ፡ ሁሉ ፡
ይጋርዳቸዋል ።

# መጽሐፈ ፡ ጥበብ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

በኢየሩሳሌም ፡ የነገሠ ፡ የዳዊት ፡ ልጅ ፡ የሰሎ
ሞን ፡ ጥበቡ ፡ ይህ ፡ ነው ።
፩፤ ይህን ፡ ዓለም ፡ የምትገዙ ፡ መኳንንት ፡ ጥበ
ብን ፡ ውደዷት ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ኃይል ፡
አስቡ ፡ በበጎ ፡ እውቀት ፡ በሰፋ ፡ ልቡና ፡ ፈል
ጉት ።
፪፤ በማይፈታተኑት ፡ ሰዎች ፡ ዘንድ ፡ እርሱ ፡ ይገ
ኛልና ። በማይክዱት ፡ ሰዎችም ፡ ዘንድ ፡ ይገለ
ጣልና ፡ ፈልጉት ።
፫፤ ጠማማ ፡ ልቡና ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ይርቃልና ፡
የተፈተነች ፡ ኃይል ፡ አላዋቆችን ፡ ዘልፋቻዋ
ለች ።
፬፤ ዲያብሎስ ፡ በተተነኰላት ፡ ሰውነት ፡ ጥበብ ፡
አታድርምና ። ለኃጢአት ፡ በተገዛ ፡ ሰውነትም ፡
አታድርምና ።
፭፤ ምክር ፡ እዝናትን ፡ የሚገልጽ ፡ የከበረ ፡ መን
ፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ክፉ ፡ የሚሆን ፡ የዲያብሎስን ፡
ትምርት ፡ ያርቃልና ፡ ከላዋቆችም ፡ ልቡና ፡
ዲያብሎስን ፡ ድል ፡ ነሥቶ ፡ ይሄዳልና ፡ በመጣ ፡
ጊዜ ፡ ክፉ ፡ የሚሆን ፡ ዲያብሎስን ፡ ይዘልፈ
ዋል ።
፮፤ ጥበብን ፡ የሚገልጽ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ሰው ፡
ወዳጅ ፡ ነውና ፡ በከንፈሩ ፡ የሚሳደበውን ፡
ከፍዳ ፡ አያነፃውም ። እግዚአብሔር ፡ በኵላሊ
ታቸው ፡ በሚያጤሱት ፡ ነገር ፡ ምስክር ፡ ነውና ፡
ነዋሪ ፡ ጉበኛ ፡ የሚሆን ፡ እርሱ ፡ ልቡናውን ፡
ይመረምረዋል ፡ ባንደበቱም ፡ የተናገረውን ፡
ነገር ፡ ይሰማዋል ።
፯፤ የእግዚአብሔር ፡ ሕይወቱ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡
በዓለም ፡ መልቷልና ። ዓለም ፡ ሁሉ ፡ የፈጠረ ፡
እርሱ ፡ ነገራቸውን ፡ ፈጽሞ ፡ ያውቃልና ።
፰፤ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ከሚነገር ፡ ከሐሰት ፡ ነገራቸው ፡
ምንምን ፡ ከርሱ ፡ አይሠወርም ።
፱፤ በልቡናቸው ፡ በመከሩት ፡ ምክር ፡ ሕገ ፡ እግዚ
አብሔርን ፡ የዘነጉ ፡ ሰዎችን ፡ የሚመረምራ
ቸው ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የተናገሩትም ፡ ነገራቸው ፡
በኃጢአታቸው ፡ ዘለፋ ፡ ሊሆንባቸው ፡ ወደ ፡
እግዚአብሔር ፡ የሚደርስ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ሥራ
ውን ፡ መግለጽ ፡ በፍርድ ፡ አይተላለፈውምና ፡
ምንምን ፡ ከርሱ ፡ አይሠወርም ።

፲፡ ስለ ፡ መቅናትም ፡ ሥራውን ፡ ሁሉ ፡ የሚሰማ ፡
አይደለምና ፡ የሚያንጐራጕሩትም ፡ ነገር ፡
ከርሱ ፡ አይሠወርም ፡፡
፲፩፡ ከማይረባ ፡ እንጉርጉሮ ፡ ተጠበቁ ፡ ከሐሜትም ፡
እንደበታችሁን ፡ ከልክሉ ፡ ቀስ ፡ ብለው ፡ የተ
ናገሩት ፡ ነገር ፡ በከንቱ ፡ አይነገርምና ፡ እንዲ ፡
ፍላፃም ፡ የሚወጋ ፡ ሐሰት ፡ የሚናገር ፡ አፍ ፡
ሰውነት ፡ ይጐዳልና ፡፡
፲፪፡ አንደበታችሁን ፡ ከሐሜት ፡ ከልክሉ ፡ ሕይወ
ታችሁ ፡ እግዚአብሔርን ፡ በመሻት ፡ ለሞት ፡
አትቅኑት ፡፡
፲፫፡ እግዚአብሔር ፡ ሞትን ፡ አልፈጠረምና ፡ ነዋሪ ፡
ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ፍጥረትን ፡ ፈጥሯልና ፡ የሰዎች ፡
ጥፋት ፡ ደስ ፡ አያሰኘውምና ፡፡
፲፬፡ በጃችሁ ፡ ሥራ ፡ ሞትን ፡ አታምጡ ፡ የሰውም ፡
መፈጠር ፡ ለድኅነት ፡ ነውና ፡ በነርሱ ፡ ዘንድ ፡
ሁሉን ፡ የሚያጠፋ ፡ የሞት ፡ መርዝ ፡ ኃጢአት ፡
አልነበረምና ፡ ሕይወት ፡ የማታልፍ ፡ ስለ ፡ ሆነች ፡፡
፲፭፡ ለመቃብርም ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ግዛት ፡ አልነበ
ረምና ፡፡
፲፮፡ እግዚአብሔርን ፡ የዘነጉ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ በቃል ፡
ጠሩት ፡ በልንጀራም ፡ አደረጉት ፡ በዚሁም ፡
ጠፉ ፡፡
፲፯፡ የርሱ ፡ ወገን ፡ መሆን ፡ ይገባቸዋልና ፡ ከርሱ ፡
ጋራ ፡ መሐላን ፡ ተማማሉ ፡፡

ምዕራፍ ፡ ፪ ፡፡

፩፡ የቀና ፡ ነገር ፡ ሳያስቡ ፡ በአእምሮዋቸው ፡
እንዲህ ፡ አሉ ፡ እነዋወራችን ፡ ጥቂት ፡ ነውና ፡
የሚያሳዝንም ፡ ነውና ፡፡
፪፡ ለሰውም ፡ ሞት ፡ መድኃኒት ፡ የለውምና ፡ የታ
ወቀም ፡ ሆኖ ፡ ከመቃብር ፡ የተመለሰ ፡ የለምና ፡፡
እኛ ፡ ግን ፡ በከንቱ ፡ ተፈጥረናልና ፡ ከተፈጠር
ንም ፡ በኋላ ፡ እንዳልተፈጠርን ፡ እንሆናለንና ፡
በፍንጫችን ፡ ያለ ፡ ትንፋሻችንም ፡ እንደ ፡ ጢስ ፡
ነውና ፡፡ ልቡናችንን ፡ በማንዋወጥ ፡ ያለች ፡
ሰውነታችንም ፡ እንደ ፡ ምጣድ ፡ ብልጭል
ጭታ ፡ ናትና ፡፡
፫፡ ነፍሳችን ፡ ከሰውነታችን ፡ ከተለየች ፡ በኋላ ፡
ትቢያ ፡ ይሆናል ፡ ሰውነታችንም ፡ እንደ ፡ ጉም ፡
ሽንት ፡ ይበተናልና ፡፡
፬፡ ስማችንም ፡ በሞትንበት ፡ ወራት ፡ ይዘነጋልና ፡
ማንማን ፡ ሥራችንን ፡ የሚያስበው ፡ የለምና ፡
እነዋወራችንም ፡ እንደ ፡ ዳመና ፡ ያልፋልና ፡
እንደሚበትን ፡ ጉምም ፡ ነውና ፡ ከፀሐይ ፡ አሻር ፡
ከዋዕዩም ፡ የተነሣ ፡ እንደ ፡ ረቂቅ ፡ ውርጭ ፡
ሆኗልና ፡፡
፭፡ እነዋወራችንም ፡ እንደ ፡ ጥላ ፡ ያልፋልና ፡ ይህ ፡
የተዘጋጀ ፡ ስለሆነ ፡ በሞታችን ፡ መክልከል ፡
የለውም ፡ ማንማንም ፡ አይመለሰውምና ፡፡
፮፡ኑ ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ እናድርግ ፡፡ በሕፃንነታችን ፡
ወራት ፡ ሳለን ፡ ከዚህ ፡ ይህ ፡ ቀረን ፡ በማለት ፡
በሰውነታችን ፡ ደስ ፡ የሚያሰኘንን ፡ ሥራ ፡
እናድርግ ፡፡
ብዙ ፡ ወይንንም ፡ እንጠጣ ፡ የሚሸት ፡ ሽቱንም ፡ ፯፡
እንቀባ ፡ ደመና ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ አይለፈን ፡፡
ሰውነታችን ፡ ሳይጠፋ ፡ ተድላ ፡ ደስታን ፡ እና ፰፡
ድርግ ፡፡ በትዕቢታችን ፡ ከምናደርገው ፡ ተድላ ፡
ደስታ ፡ አንድ ፡ የማይሆን ፡ ሰው ፡ ማንማን ፡
አይኑር ፡፡
ከኛ ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ የማይገባው ፡ ሰው ፡ አይ ፱፡
ኑር ፡ በየጊዜው ፡ ይህን ፡ አንተው ፡ እርሱ ፡ ዕድ
ላችን ፡ ነውና ፡ ይኸውም ፡ ርስታችን ፡ ነውና ፡
የስንፍናን ፡ ነገር ፡ ሥርዓት ፡ አድርገን ፡ እናኑር ፡
እውነተኛውን ፡ ደኃ ፡ እንቀማ ፡ ለባልቴትም ፡ ፲፡
እንራራ ፡፡ ቀኑ ፡ ዘመኖቹ ፡ ብዙ ፡ ከሆነ ፡
ከሽማግሌው ፡ ሽበት ፡ የተነሣ ፡ አንፈር ፡፡
እንሥረቅ ፡ እንቀማ ፡ የማይል ፡ ልቡና ፡ ደካማ ፡ ፲፩፡
ይብላልና ፡ የቀና ፡ ነገርን ፡ ሳያስቡ ፡ በአእምሮ
ዋቸው ፡ ይህ ፡ ቅሚያችን ፡ እውነተኛ ፡ ሕግ ፡
ይሁነን ፡ አሉ ፡፡
የበሕርይ ፡ አምላክ ፡ ክርስቶስን ፡ ኑ ፡ እንግደ ፲፪፡
ለው ፡ አሉ ፡ በኛ ፡ ጭንቅ ፡ የጸና ፡ ሆኖብናልና ፡
ሥራችንንም ፡ ይቃወመዋልና ፡ ሕግ ፡ በማጣ
ታችን ፡ ያሽሟጥጠናልና ፡ የትምህርታችን ፡
በደልነቱን ፡፡
እግዚአብሔርንም ፡ ማወቅ ፡ በኔ ፡ አለ ፡ ይላልና ፡ ፲፫፡
የእግዚአብሔርም ፡ ልጅ ፡ ነኝ ፡ ይላልና ፡፡
ልቡናችንንም ፡ የሚዘልፍ ፡ ሆኗልና ፡፡ ፲፬፡
በመልአኩ ፡ በኛ ፡ ጭንቅ ፡ ሆኖብናልና ፡ እነዋ ፲፭፡
ወሩም ፡ ከፍጡራን ፡ ጋራ ፡ አይመሳሰልምና ፡
ሥራውም ፡ ልዩ ፡ ነውና ፡፡
በርሱ ፡ ዘንድም ፡ የተናቅን ፡ ሆነናልና ፡ ከኃጢ ፲፮፡
አት ፡ እንዲርቁ ፡ ከሥራችንም ፡ ይርቃልና ፡፡ የጸ
ጋግ ፡ ሰዎች ፡ መጨረሻቸውን ፡ ያመሰግናልና ፡
እግዚአብሔርም ፡ አባቱ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ይመካ
ልና ፡ ኑ ፡ እንግደለው ፡ አሉ ፡፡
ነገሩም ፡ ቀዋሚ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እንይ ፡ ከመልኩ ፡ ፲፯፡
ማግር ፡ የተነሣ ፡ በመከራ ፡ እንፈትነው ፡ አሉ ፡፡
የእግዚአብሔር ፡ ደገኛ ፡ የበሕርይ ፡ ልጅ ፡ ከሆነ ፡ ፲፰፡
ያድነው ፡ ከሚቃወሙትም ፡ ሰዎች ፡ እጅ ፡
ያድነው ፡፡
ቅንነቱን ፡ እናውቅ ፡ ዘንድ ፡ እየሰደብን ፡ በመ ፲፱፡
ከራ ፡ እንመርምረው ፡፡
እንደ ፡ ቃሉ ፡ ረዳት ፡ ይሆነው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ፳፡
የከፋ ፡ የተዋረደ ፡ ሞትን ፡ እንፍረድበት ፡ አሉ ፡፡
ይህን ፡ ነገር ፡ አሰቡ ፡ ክፋታቸው ፡ የልብ ፡ ስው ፳፩፡
ሮች ፡ አድርጋቸዋለችና ፡ በዚህም ፡ ሳቱ ፡፡
እግዚአብሔር ፡ ሰውሮ ፡ ለጻድቁ ፡ የሚሰጠ ፳፪፡
ውን ፡ አላወቁም ፡ ደግ ፡ ሰው ፡ የሚያገኘውን ፡
ዋጋ ፡ ተስፋ ፡ አላደረጉም ፡፡
በርሱ ፡ አምሳል ፡ ያለ ፡ ኃጢአት ፡ ሰውን ፡ ፈጥ ፳፫፡
ሮታልና ፡ ነውር ፡ የሌለባቸው ፡ ንጹሐት ፡ ነፍ
ሳት ፡ የሚቀበሉት ፡ ብዙ ፡ ክብርን ፡ አላወቁም ፡፡
በዲያብሎስ ፡ ቅንዓት ፡ ሞት ፡ መጣ ፡ ወደዚህ ፡ ፳፬፡
ዓለምም ፡ ገባ ፡፡
ከዚህ ፡ ከዲያብሎስ ፡ እድል ፡ የሆነችን ፡ ሰዎች ፡ ፳፭፡
ይፈትናል ፡፡

ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ የደጋግ ፡ ሰዎች ፡ ነፍስ ፡ ግን ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ እጅ ፡ ናት ፡ የኃጢአተኞች ፡ መከራ ፡ አላ
ገኛቸውም ።
፪ ሰላጥቆች ፡ ዓይኖች ፡ ግን ፡ የሞቱ ፡ መሰሉ ፡ በሞ
ትም ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ መውጣታቸው ፡ ክፋት ፡
እንዳለባቸው ፡ ተቆጠረ ።
፫ ሞታቸውም ፡ ጥፋት ፡ መሰለ ፡ እነርሱ ፡ ግን ፡
በተድላ ፡ በደስታ ፡ አሉ ።
፬ በሰው ፡ ፊት ፡ ሞቱ ፡ ቢባል ፡ አለኝታቸው ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ሞት ፡ የሌለበት ፡ ፍጽ
ምት ፡ ሕይወት ፡ ናት ።
፭ ጥቂት ፡ መከራ ፡ ተቀብለው ፡ በብዙ ፡ ክብር ፡
ይዘጋጃሉ ። እግዚአብሔር ፡ ፈትኗቸዋልና ፡ እነ
ርሱ ፡ የተገቡ ፡ ሆነው ፡ አገኛቸው ።
፮ ወርቅ ፡ በጎዶ ፡ እንዲፈተን ፡ በመከራ ፡ ፈትኖ ፡
የአሮንን ፡ ዕጣን ፡ እንደ ፡ ተቀበለ ፡ እንደዚያ ፡
ተቀበላቸው ።
፯ በክብር ፡ በሚጐበኙበትም ፡ ወራት ፡ እንደ ፡
ፀሐይ ፡ ያበራሉ ፡ በብር ፡ ላይ ፡ የወደቀ ፡ የብረት ፡
ፍንጣሪ ፡ እንዲሰፋ ፡ በክብር ፡ እየሰፉ ፡ ይሄዳሉ ።
፰ ሕዝቡን ፡ አሕዛቡን ፡ ይገዛሉ ፡ እግዚአብሔ
ርም ፡ ለዘለዓለም ፡ ይነግሥላቸዋል ።
፱ በርሱ ፡ የሚያምኑ ፡ ሰዎች ፡ የቀና ፡ ሕጉን ፡ ይወ
ድዳሉ ። ጸጋ ፡ ክብር ፡ ለወዳጆቹ ፡ ነውና ፡ የጐ
ላም ፡ መጐብኘት ፡ ለወዳጆቹ ፡ ነውና ፡ ወዳጆቹ ፡
እነዚህ ፡ በርሱ ፡ ፍቅር ፡ ጸንተው ፡ ይኖራሉ ።
፲ እግዚአብሔርን ፡ የዘነጉ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ እን
ዳሰቡ ፡ ክፉ ፡ ፍርድን ፡ ያገኛሉ ፡ በጎ ፡ ሥራን ፡
ያቀለሉ ፡ ሰዎች ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ራቁ ።
፲፩ ጥበብን ፡ ምክር ፡ ዕዝናትን ፡ የሚንቁ ፡ ሰዎች ፡
ጐስቋሎች ፡ ናቸው ። አለኝታቸውም ፡ ከንቱ ፡
ነው ፡ ድካማቸውና ፡ መከራቸውም ፡ ጥቅም ፡ የሌ
ለው ፡ ነው ።
፲፪ ሥራቸውም ፡ ከንቱ ፡ ነው ፡ ሚስቶቻቸውም ፡
አላዋቆች ፡ ናቸው ፡ ልጆቻቸውም ፡ ጠማሞች ፡
ናቸው ።
፲፫ ትውልዳቸውም ፡ የተረገመ ፡ ነው ፡ ነውር ፡
ነቀፋ ፡ የሌለበት ፡ የኃጢአት ፡ ምንጣፍ ፡ የማ
ታውቅ ፡ መካን ፡ ሴት ፡ የተደነቀች ፡ ከኃጢአት ፡
የነፃች ፡ ናትና ፡ ይህች ፡ እንዲህ ፡ ያለችው ፡ ሴት ፡
ነፍሳት ፡ በሚጐበኙበት ፡ ጊዜ ፡ ዋጋዋን ፡ ታገኛ
ለች ።
፲፬ የተመረጠች ፡ የሃይማኖት ፡ ዋጋ ፡ ይሰጠዋልና ፡
በሚወደድ ፡ በእግዚአብሔርም ፡ ቤት ፡ ዕድሉ ፡
ይሰጠዋልና ፡ በበለ ፡ ዘሩ ፡ ኃጢአት ፡ ያልሠራ ፡
በእግዚአብሔርም ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ያላሰበ ፡
ጃንደረባም ፡ ዋጋውን ፡ ያገኛል ።
፲፭ የደግ ፡ ሰው ፡ የድካሙ ፡ ዋጋ ፡ ክብር ፡ ነውና ፡
የነፍስም ፡ ጌጥ ፡ ነው ፡ በውቀት ፡ ለጸና ፡ አባት
ነቱ ፡ ጥፋት ፡ የለበትም ።
፲፮ ያመንዝራ ፡ ልጆች ፡ ግን ፡ ከቊጥር ፡ የጐደሉ ፡
ይሆናሉ ። ሕግ ፡ ተላልፎ ፡ ከኃጢአት ፡ ምንጣፍ ፡
የተወለደ ፡ ልጅም ፡ ይጠፋል ።
በዚህም ፡ ዓለም ፡ አነዋወራቸው ፡ ምንም ፡ ቢበዛ ፡ ፲፯
ምንም ፡ ከመኖር ፡ አይቈጠርም ፡ አባትነታቸ
ውም ፡ በፍጻሜያቸው ፡ የጐሰቈለ ፡ ይሆናል ።
ፈጥነው ፡ ቢሞቱ ፡ ኃጢአታቸው ፡ በተመረመ ፲፰
ረበት ፡ ቀን ፡ አለኝታ ፡ መረጋጋት ፡ የላቸውም ።
የበደለኛ ፡ ልጅ ፡ ፍጻሜዋ ፡ ክፉ ፡ ነውና ። ፲፱

ምዕራፍ ፡ ፬ ።

ከበጎነት ፡ ጋራ ፡ ያለ ፡ አለመውለድ ፡ ፍጹም ፡ ፩
ሥራ ፡ ነው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የታወ
ቀች ፡ ስለ ፡ ሆነች ፡ ስም ፡ አጠራሯም ፡ ሕይ
ወት ፡ ነው ።
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሳለች ፡ በሰው ፡ ዘንድ ፡ ያከብሯ ፪
ታል ፡ ከሞተችም ፡ በኋላ ፡ ፈጽመው ፡ ይወዷ
ታል ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ኃጢአትን ፡ ድል ፡ የመ
ንሣቷን ፡ ዋጋ ፡ የማያልፍ ፡ ክብርን ፡ አግኝታ ፡
በወዲያ ፡ ዓለም ፡ ትኖራለች ።
እግዚአብሔርን ፡ የዘነጉ ፡ ሰዎች ፡ ልጆች ፡ ፫
ብዛት ፡ አይረባም ፡ የክፉ ፡ ልጅ ፡ አባት ፡ እናቷ ፡
በደግነት ፡ አይታወቅም ፡ ጽኑ ፡ አነዋወርንም ፡
አታደርግም ።
ከልጆቿም ፡ ጽኑ ፡ ልጅ ፡ ቢወለድ ፡ ሳያድግ ፡ ፬
ሞት ፡ ያጠፋዋል ፡ በሞት ፡ ሥልጣንም ፡ ይጠ
ፋል ።
ልጆቿ ፡ እካለ ፡ መጠን ፡ ሳያደርሱ ፡ ያጠፋሉ ። ፭
ጊዜው ፡ አይደለምና ፡ ልጃቸውም ፡ ለመሥዋዕ
ትነት ፡ የማይገባ ፡ ከንቱ ፡ ልጅ ፡ ነው ።
ለምንም ፡ ለምንም ፡ አይረባም ፡ ከክፉ ፡ ሰዎች ፡ ፮
የሚወለዱ ፡ ልጆችም ፡ በኃጢአታቸው ፡ በተ
መረመሩ ፡ ጊዜ ፡ ለናት ፡ አባታቸው ፡ ክፋት ፡
ምስክሮች ፡ ናቸው ።
ደግ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ለመሞት ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ ፯
በዕረፍት ፡ ይኖራል ።
የእድግና ፡ መከበር ፡ በቀን ፡ ብዛት ፡ በዘመኖ ፰
ችም ፡ ቍጥር ፡ አይደለም ።
ሽበትስ ፡ የሰው ፡ ዕውቀቱ ፡ ነው ፡ የዕርግናም ፡ ፱
ዘውዱ ፡ ያለ ፡ ነውር ፡ መኖር ፡ ነው ።
እግዚአብሔርን ፡ የሚወድ ፡ ሰው ፡ ይወደዳል ፡ ፲
በኃጢአተኞች ፡ መካከል ፡ ሳለም ፡ በሞት ፡ ይሄ
ዳል ።
ክፋት ፡ ዕውቀትን ፡ ሳትለውጥበት ፡ ይህም ፡ ፲፩
ባይሆን ፡ ሐሰት ፡ ሰውነቱን ፡ ሳታስትበት ፡
በሞት ፡ ተነጥቆ ፡ ይሄዳል ።
የክፋት ፡ ቅንዓት ፡ በጎ ፡ ሥራዎችን ፡ ያጠፋልና ፡ ፲፪
ወጪ ፡ ወራጅ ፡ ፈቃድም ፡ የዋህ ፡ ልቡናን ፡
ያሳዝናልና ፡ በሞት ፡ ፈጥኖ ፡ ይሄዳልና ።
ሰውነቱ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የተወደደች ፡ ፲፫
ሆናለችና ፡ በጥቂት ፡ ዘመንም ፡ ቢሞት ፡ ብዙ ፡
ዘመን ፡ ጨረሰ ።
ስለዚህም ፡ ነገር ፡ ኃጢአት ፡ ከሚሠራበት ፡ ፲፬
ከዚህ ፡ ዓለም ፡ በሞት ፡ ቸኩሎ ፡ ሄደ ፡ ይህን ፡
ግን ፡ ልዩ ፡ የሆኑ ፡ ሰዎች ፡ አይተው ፡ ልብ ፡ አላ
ደረጉትም ።

፲፭ የእግዚአብሔር ፡ ፍርዱ ፡ ለወዳጆቹ ፡ ነውና ፡
በይቅርታውም ፡ መጐብኘቱ ፡ ለመረጣቸው ፡
ሰዎች ፡ ነውና ።
፲፮ የዚህን ፡ ትርጓሜ ፡ በልቡናቸው ፡ አላሳደሩ
ትም ። ደግ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ በደ
ጎነቱ ፡ ሳሉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የዘነጉ ፡ ሰዎ
ችን ፡ ይገዛል ። ጐልማሳ ፡ ሰውም ፡ ፈጥኖ ፡
በሞተ ፡ ጊዜ ፡ በደል ፡ በተደረገበት ፡ የዕርግና ፡
ዘመናቸው ፡ የበዛ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የዘነጉ ፡
ሰዎችን ፡ ይገዛል ።
፲፯ ብልህ ፡ የሆነ ፡ የደጉን ፡ ሰው ፡ ሞት ፡ አይተው ፡
ልብ ፡ አያደርጉትምና ፡ ስለርሱም ፡ ምንምን ፡
እንደ ፡ መከረ ፡ እግዚአብሔርም ፡ ወደርሱ ፡
ለምንም ፡ ለምንም ፡ እንደ ፡ ቀረበው ፡ አያውቁ
ምና ፡ አይተው ፡ ይጠቃቀሱበታል ።
፲፰ እሳቸውን ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ይስቅባቸዋል ።
፲፱ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ለጐሰቈለ ፡ ሞት ፡ ይሆናሉ ፡
ለዘለዓለምም ፡ ሙታን ፡ ለሚሰድቡት ፡ ስድብ ፡
ይሆናሉ ፡ ነፍሳቸውን ፡ ከሥጋቸው ፡ ፈጽሞ ፡
ይለያቸዋልና ፡ ቃል ፡ ሳይናገራቸው ፡ በፊታ
ቸው ፡ የወደቁ ፡ ሆነው ፡ ይገኛሉ ። ከበትነታ
ቸው ፡ ያውከቸዋል ፡ ለዘለዓለሙ ፡ እንደ ፡
ምድረ ፡ በዳ ፡ ምድር ፡ ይሆናሉ ። የተጨነቁም ፡
ይሆናሉ ፡ ስም ፡ አጠራራቸውም ፡ ይጠፋል ።
፳ የፈሩ ፡ ሆነው ፡ በኃጢአታቸው ፡ ለመወቀስ ፡
ይቀርባሉ ፡ ኃጢአታቸውም ፡ ተገልጾ ፡ በፊታ
ቸው ፡ ሆኖ ፡ ይዘልፋቸዋል ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

፩ መከራ ፡ በጸኑበት ፡ ድካሙንም ፡ በከዱ ፡ ደተ
ናገረው ፡ ወንጌልንም ፡ በናቁ ፡ በአይሁድ ፡ ፊት ፡
ያን ፡ ጊዜ ፡ ክርስቶስ ፡ በብዙ ፡ መገለጥ ፡ ይቆመ
ጣል ።
፪ በክፉ ፡ ማስፈራትና ፡ በግርማ ፡ ሆኖ ፡ ባዩት ፡
ጊዜ ፡ ይታወካሉ ፡ ድንቅ ፡ ስለሚሆን ፡ ትንግሌ
ውም ፡ ይደነቃሉ ።
፫ እያዘኑም ፡ በጨነቀም ፡ ልቡና ፡ እየተከዙ ፡
ይጮሁ ፡ ቀድሞ ፡ በሰነፎች ፡ በኛ ፡ ዘንድ ፡ መሳ
ቂያን ፡ ማሽሟጠጫን ፡ የሆነው ።
፬ ሥራውንም ፡ ስንፍና ፡ ሞቱንም ፡ የተናቀ ፡ ያደ
ረግንበት ፡ ይህ ፡ ነውን ፡ ይላሉ ።
፭ እስበሳቸው ፡ እንዴት ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡
ሆነ ፡ ርስቱ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያትስ ፡ እንዴት ፡
በሐዋርያት ፡ ሆነች ።
፮ ከቀና ፡ ሕግ ፡ ወጥተን ፡ ሳትን ፡ የክርስቶስ ፡ ብር
ሃን ፡ ረድኤት ፡ አልተገለጠልንም ፡ ክርስቶስም ፡
ለኛ ፡ አልተወለደልንም ።
፯ ጥፋትና ፡ ክህደትን ፡ በሥራችን ፡ መላንም ፡ ክጻ
ድቃን ፡ ከምድረ ፡ በዳ ፡ ወደ ፡ ሆነች ፡ ወደ ፡ ገሃ
ነምም ፡ ተፈርዶብን ፡ ሄድን ። የእግዚአብሔር
ንም ፡ ሕግ ፡ አላወቅንም ።
፰ ይህ ፡ ትዕቢት ፡ ምን ፡ ጠቀመን ፡ ከትዕቢት ፡
ጋራ ፡ ያለ ፡ የአሪትስ ፡ በለጠግነት ፡ ምን ፡ አመ
ጣልን ።

ይህ ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ጥላ ፡ አላፊ ፡ ኖሮ ፡ ፈጥኖ ፡ ፱
እንደሚጠፋ ፡ ወሬ ፡ እንደሚሄድ ።
ውኃ ፡ በምላቱ ፡ እንደሚነጥቀው ፡ ያለፈበት ፡ ፲
መንገዱም ፡ እንደማይገኝ ፡ በማዕበሉ ፡ መካከል ፡
አካሉ ፡ የሄደበት ፡ መንገድ ፡ እንዳይገኝ ፡ መር
ከብ ።
በነፋስ ፡ መካከል ፡ የሚሄድ ፡ ዎፍ ፡ የሄደበት ፡ ፲፩
ፍለጋው ፡ እንዳይገኝ ። በበረረ ፡ ጊዜ ፡ ቀሊል ፡
ነፋስን ፡ የተከተለ ፡ አድርጎታልና ፡ ፈጥኖም ፡
በመሄዱ ፡ ይከፍለዋልና ፡ ክንፉን ፡ ስብርብር ፡
አድርጎ ፡ ፈጥኖ ፡ ይሄዳልና ፡ ከሄደም ፡ በኋላ ፡
በነፋሱ ፡ ውስጥ ፡ የሄደበት ፡ ምልክቱ ፡ እንደማ
ይገኝ ።
ይህም ፡ ባይሆን ፡ የታወረወረ ፡ ፍላፃም ፡ ነፋስ ፡ ፲፪
ተከፍሎበታልና ፡ በጊዜዋ ፡ ጊዜ ፡ ተመልሶ ፡
እንደ ፡ ቀድሞው ፡ ሆኗልና ፡ በነፋሱ ፡ ውስጥ ፡
የሄደበት ፡ እንዳይታወቅ ።
እንደዚሁ ፡ እኛም ፡ በተነሣን ፡ ጊዜ ፡ ጠፋን ። ፲፫
በክፋታችን ፡ ጠፋን ፡ እንጂ ፡ በጎ ፡ ምልክትን ፡ ፲፬
እናይ ፡ ዘንድ ፡ አልተገባንም ። (አሥረ ፡ ርግዘ
ቱን ፡)
እግዚአብሔርን ፡ የሚዘነጉ ፡ ሰዎች ፡ አለኝታ ፲፭
ቸው ፡ ነፋስ ፡ እንደሚበትነው ፡ ትቢያ ፡ በነፋስ ፡
እንደ ፡ ረቂቅ ፡ ውርጭም ፡ በነፋስ ፡ እንደሚ
ጠፋ ፡ እንደ ፡ ጢስም ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ አድሮ ፡
እንደሚሄድ ፡ መጻተኛ ፡ ስመ ፡ አጠራር ፡ ነውና ፡
በክፋታችን ፡ ጠፋን ፡ እንጂ ፡ በጎ ፡ ምልክትን ፡
እናይ ፡ ዘንድ ፡ አይገባንም ።
ደግ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ የቀኑ ፡ ሆነው ፡ ለዘለዓለም ፡ ፲፮
ይኖራሉ ፡ በእግዚአብሔርም ፡ ዘንድ ፡ ዋጋ
ቸው ፡ የጸና ፡ ነው ፡ አሳባቸውም ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ ዘንድ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ።
በሥልጣኑ ፡ ይሠውራቸዋልና ፡ በኃይሉም ፡ ፲፯
ይረዳቸዋልና ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ክብር ፡ ያለው ፡
መንግሥትን ፡ ጌጥ ፡ ያለው ፡ አክሊልን ፡ ከእግ
ዚአብሔር ፡ እጅ ፡ ይቀበላሉ ።
ለአምልኮቱ ፡ የቀናበት ፡ የሚጻ ፡ ጸብቱን ፡ ፲፰
ፈጽሞ ፡ ይይዛል ፡ ጠላቶቹን ፡ ለመበቀል ፡
(ግብጻውያን ፡) ፍጥረቱን ፡ የሚጻ ፡ ጸብት ፡
ያደርጋታል ። (ኤርትራ ፡)
የውነተኛ ፡ ጥሩርንም ፡ ይለብሳል ፡ ማድላት ፡ ፲፱
የሌለበት ፡ በርበርቱን ፡ ይደፋል ።
የማይሸነፍ ፡ የውነተኛ ፡ ጋሻንም ፡ ይይዛል ። ፳
የሚቆርጥ ፡ መዓቱ ፡ ሰይፍን ፡ ያስላል ፡ ሙሴ ፡ ፳፩
ከእግዚአብሔር ፡ ጋራ ፡ ሆኖ ፡ ግብጻውያንን ፡
ተጣልቶ ፡ ይዋጋል ።
ፈጥኖ ፡ ያገኛቸው ፡ ዘንድ ፡ በሳቱ ፡ በግብጻው ፳፪
ያን ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ መብረቅ ፡ የሚያስፈራ ፡
መዓቱ ፡ በደል ፡ ነጐድ ፡ ቀንቶ ፡ ይሄድባቸዋል ።
ጻድቃን ፡ እስራኤል ፡ ግን ፡ እንዳማረ ፡ ቀስት ፡
ደመና ፡ አከባበብ ፡ ከበው ፡ ረድኤቱን ፡ በማግ
ኘት ፡ ያመሰግናሉ ።
ከመዓቱም ፡ በደል ፡ ነጐድ ፡ ደንጊያም ፡ ፈጥኖ ፡ ፳፬
በረዶ ፡ ያወርዳል ። የበሕሩም ፡ ውኃ ፡ በሳቸው ፡

ይበሳጭባቸዋል ፡ ፈሳሾችም ፡ ተነዋውጠው ፡
ፈጥነው ፡ ይከቧቸዋል ።
፳፬ ኃይል ፡ ያለው ፡ ነፋስ ፡ ይቃወማቸዋል ፡ ነፋስ ፡
እንደ ፡ መሆኑ ፡ ድርቅ ፡ ያደርጋቸዋል ፡ ኃጢ
አት ፡ ምድሩን ፡ ሁሉ ፡ ታጠፋለችና ፡ ክፋም ፡
መሥራት ፡ የኃያላኑን ፡ ዙፋን ፡ ያጠፋልና ፡
ይበትናቸዋል ።

ምዕራፍ ፡ ፮ ።

፩ የዚህ ፡ ዓለም ፡ ነገሥታት ፡ ስሙ ፡ የምድር ፡
ዳርቻን ፡ የምትገዙ ፡ መኳንንትም ፡ ልብ ፡ አድ
ርጋችሁ ፡ እወቁ ።
፪ ምድርን ፡ የምትገዙ ፡ በሠራዊትም ፡ ብዛት ፡
የምትታበዩ ፡ ስሙ ።
፫ እግዚአብሔር ፡ ጽንዕን ፡ ሰጥቷችኋልና ፡ ይህም ፡
ጽናችሁ ፡ ከልዑል ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡
የተገኘ ፡ ነውና ፡ ምግባራችሁንም ፡ የሚመረ
ምራችሁ ፡ እርሱ ፡ ነውና ፡ ምክራችሁንም ፡
መርምሮ ፡ ያውቃልና ።
፬ እናንተ ፡ እውነት ፡ የምትፈርዱ ፡ መልክተኞች ፡
ስትሆኑ ፡ የቅና ፡ ፍርድን ፡ እንዴት ፡ አትፈርዱ ፡
ሕጉንስ ፡ እንዴት ፡ አልጠበቃችሁ ፡ በእግዚአ
ብሔር ፡ ሥራ ፡ እንዴት ፡ ጸንታችሁ ፡ አልኖራ
ችሁ ፡ ተብሎ ፡ ይፈረድባችኋልና ፡ ስሙ ።
፭ ፈጥኖ ፡ የሚቃወማችሁ ፡ ድንጋፄ ፡ በላያችሁ ፡
ያመጣል ፡ ለመኳንንቱ ፡ የተቆረጠ ፡ ፍርድ ፡
ያደረጋልና ።
፮ ለደኃው ፡ ግን ፡ ሥላሴ ፡ ከቸርነት ፡ ሥራ ፡ የተ
ነሣ ፡ ያቃልሉለታል ። ኃይለኞች ፡ ሰዎችን ፡
ግን ፡ ጽኑ ፡ ምርመራ ፡ ይመረምሯቸዋል ።
፯ ፡ ፰ እግዚአብሔር ፡ ታናሹና ፡ ታላቁን ፡ ስለ ፡ ፈጠረ ፡
እግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ አይቶ ፡ አያደላምና ።
የባለጸጋውን ፡ መክበር ፡ አያፍርምና ፡ እንደዚ
ሁም ፡ አስቦ ፡ ገዢውንም ፡ ተገዢውንም ፡ ይሠ
ራራቸዋል ።
፱ በባለጸጎች ፡ ግን ፡ ጽኑ ፡ ምርመራ ፡ ይደርስባቸ
ዋል ።
፲ ክፉ ፡ የምትሆኑ ፡ ሰውንም ፡ የምትበድሉ ፡ መኳ
ንንት ፡ ሆይ ፡ ጥበቤን ፡ ታውቁ ፡ ዘንድ ፡ በመ
ከራ ፡ እንዳትሰነካከሉ ፡ ነገሬ ፡ ለናንተ ፡ ነው ።
፲፩ እውነተኛ ፡ ትእዛዙን ፡ አውቀው ፡ የሚጠብቁ ፡
በውነት ፡ ይከብራሉና ፡ የተማሩትም ፡ ሰዎች ፡
ይቅርታን ፡ ያገኛሉና ።
፲፪ እንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ነገሬን ፡ ውደዱት ፡ ይቅር
ታን ፡ ቸርነትንም ፡ ታገኙ ፡ ዘንድ ፡ ተመከሩ ።
፲፫ ጥበብ ፡ ፈጽማ ፡ የገላች ፡ ናት ፡ ሥርዓቷም ፡
አያልፍም ፡ የሚወዷትም ፡ ሰዎች ፡ ፈጥነው ፡
ያዋቃል ፡ የሚፈልጓትም ፡ ሰዎች ፡ ያገኙአታል ።
፲፬ ለሚወዷትም ፡ ሰዎች ፡ ትደርስላቸዋለች ፡ አስ
ቀድማም ፡ ትገለጥላቸዋለች ።
፲፭ በደጃፉ ፡ ስትጠብቀው ፡ ሁልጊዜ ፡ እርሱ ፡ ያገኛ
ታልና ፡ ወደርስዋ ፡ የሚገሠግሥ ፡ ሰው ፡ አይ
ደክምም ።
፲፮ እርስዋን ፡ ማሰብ ፡ የውቀት ፡ ፍጻሜ ፡ ነውና ።
ፈጥኖ ፡ ስለርሷ ፡ የሚተጋ ፡ ሰው ፡ ያለ ፡ ኃዘን ፡
ይኖራል ።
የሚገቧትን ፡ ሰዎች ፡ ይህቺ ፡ ስትፈልጋቸው ፡ ፲፯
ትመጣለችና ። በመንገድም ፡ ድንገት ፡ ተሥላ ፡
አምራ ፡ ትታያቸዋለችና ፡ በፍጹም ፡ እውቀት ፡
ትገናኛቸዋለች ።
የዘጠኙ ፡ ቃል ፡ አበጋዝ ፡ ኢታምልክ ፡ ቀዋሚ ፡ ፲፰
ነውና ፡ እሷንም ፡ መውደድ ፡ በዚችም ፡ ሕጊ
ቱን ፡ ማስተንተን ፡ እሷን ፡ መውደድ ፡ ነውና ።
እሷንም ፡ መውደድ ፡ ሕጓን ፡ መጠበቅ ፡ ነውና ፡ ፲፱
ሕጓንም ፡ መስማት ፡ መረዳት ፡ ሕይወተ ፡ ነፍስ ፡
ነውና ።
ሕይወተ ፡ ነፍስም ፡ ሰውን ፡ ወደ ፡ እግዚአብ ፳
ሔር ፡ የቀረበ ፡ ታደርጋለችና ።
ጥበብንም ፡ መውደድ ፡ ወደ ፡ መንግሥት ፡ ታደ ፳፩
ርሳለችና ።
አሕዛብን ፡ የምትገዙ ፡ መኳንንት ፡ ዙፋንን ፡ ፳፪ ፳፫
ሹመትን ፡ መንግሥትን ፡ ከወደዳችሁ ፡ ለዘለዓ
ለሙ ፡ ትነግሡ ፡ ዘንድ ፡ ጥበብን ፡ አክብሯት ፤
ጥበብ ፡ ምንድናት ፤ እንደ ፡ ምንስ ፡ ነበረች ፡
እኔ ፡ እነግራችኋለሁ ፡ የተሠወረ ፡ምሥጢሯ
ንም ፡ ከንተ ፡ አልሠውርም ። ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡
አኳኋኗን ፡ መርምሬ ፡ እርሷን ፡ ማወቅ ፡ የተገ
ለጸ ፡ አደርጋለሁ ፡ እንጂ ፡ እውነቱን ፡ ነገር ፡
አልተላለፍም ።
ምቀኛ ፡ በሚቀናበት ፡ ቅናት ፡ ጸንቼ ፡ አልኖ ፳፬
ርም
የመምህራን ፡ ብዛት ፡ የዓለም ፡ መድኃኒት ፡ ስለ ፡ ፳፭
ሆነ ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ ከጥበብ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡
አይሆንምና ፡ ጸንቼ ፡ አልኖርም ።
አዋቂም ፡ ንጉሥ ፡ ለሠራዊቱ ፡ ጠበቃ ፡ ነውና ፡ ፳፮
በቃሌ ፡ ተመከሩ ፡ ትረባላችሁ ።

ምዕራፍ ፡ ፯ ።

እንደ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በሞት ፡ የተካከልኩ ፡ ፩
እኔ ፡ ፈራሽ ፡ ሰው ፡ ነኝና ፡ አስቀድሞ ፡ የተፈ
ጠረ ፡ የምድራዊ ፡ የአዳም ፡ ልጅም ፡ ነኝና ፡
በናቴ ፡ ማኅፀንም ፡ ሥጋ ፡ ሆኜ ፡ ተቀርጫለሁና ።
በመገናኘት ፡ ጊዜ ፡ መኝታን ፡ በመውደድና ፡ ፪
ካባት ፡ በሚከፈል ፡ ዘር ፡ አሥር ፡ ወር ፡ በደም
ነት ፡ ረግቼ ፡ ተቀምጫለሁና ።
በተፈጠርኩም ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ፫
ነፍስን ፡ ነስቻለሁና ፡ ወደ ፡ ምድርም ፡ ወርጃለ
ሁና ። ሙቼ ፡ በሚያለቅሱልኝ ፡ አምሳል ፡ አስ
ቀድሜ ፡ ልቅሶን ፡ አለቀስኩ ።
ከነገሥታት ፡ መወለዴ ፡ ልዩ ፡ የሆነ ፡ የለምና ፡ ፬ ፡ ፭
በጨርቅ ፡ ተጠቅልዬ ፡ እያነጠነጥኩ ፡ አደግሁ ።
የሰው ፡ ሁሉ ፡ ከወዲያ ፡ ዓለም ፡ ወዲህ ፡ ዓለም ፡ ፮
አመጣጡ ፡ አንዲት ፡ ናትና ፡ መወለዱም ፡ ከሁሉ ፡
የተካከለ ፡ ነውና ።
ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ለመንኩ ፡ ዕውቀት ፡ ተሰጠኝ ፡ ፯
ለመንኩ ፡ ጥበብን ፡ የሚገልጽ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡
አደረብኝ ።
ከመንግሥት ፡ አገዛዝ ፡ ከዙፋንም ፡ ይልቅ ፡ አከ ፰

በርኋት፡ በርሷ፡ ዘንድ፡ ብዕልን፡ እንደ፡ ኢምንት፡ አደረግኋት።
፱፡ ወርቅ፡ ሁሉ፡ በርሷ፡ ዘንድ፡ የተናቀ፡ ነውና፡
በርሷም፡ ብሩ፡ እንደ፡ ጭቃ፡ ነውና፡ ዋጋ፡
በሌለው፡ ዕንቍ፡ መሰልኋት።
፲፡ በደኅንነት፡ ከመኖር፡ ከደም፡ ግበትም፡ ፈጽሜ፡
ወደድኋት። ከርሷ፡ ከሚወጣ፡ ብርሃን፡ አይወ
ሰንም፡ አይጠፋምና፡ ስለ፡ ብርሃን፡ ፋንታ፡
ትሆነኝ፡ ዘንድ፡ መረጥኋት።
፲፩፡ ከርሷ፡ ጋር፡ አንድነት፡ እነዚህ፡ ሁሉ፡ ተድላ፡
ደስታዎች፡ መጡልኝ፡ ቍጥር፡ የሌለው፡ ባለ
ጠግነት፡ በርሷ፡ መጣልኝ።
፲፪፡ ይቺ፡ ጥበብ፡ የነዚህ፡ ሁሉ፡ አበጋዛቸው፡
ናትና፡ በሁሉ፡ ደስ፡ አለኝ። ከዚህ፡ አስቀድሞ፡
የነዚህ፡ ሁሉ፡ እሳባቸው፡ ጥበብ፡ እንደ፡ ሆንች፡
አላወቅሁም፡ ነበር።
፲፫፡ ይህን፡ ባወቅሁ፡ ጊዜ፡ ያለምቀኝነት፡ ያለቅናት፡
እርሷን፡ አስተምራለሁ፡ ምሥጢሯንም፡ አል
ሠውርም።
፲፬፡ ለሰውም፡ የማያልቅ፡ ድልብ፡ ናት፡ ገንዘብ፡
ያደረጓት፡ ሰዎች፡ ሁሉ፡ ከእግዚአብሔር፡
ዘንድ፡ ደርሰው፡ ሀብትን፡ የምትገልጽ፡ የም
ክር፡ ዕገዛናት፡ ሥራ፡ ስለ፡ ሆንች፡ ወዳጅ፡ ሆኑ።
፲፭፡ ለኔም፡ እግዚአብሔር፡ የሚወደውን፡ ነገር፡
እናገር፡ ዘንድ፡ ሰጠኝ። ወደ፡ ጥበብ፡ የሚመራ፡
ነውና፡ የመምህራንንም፡ ሥራ፡ የሚያቀና፡
ነውና፡ ለሚሰጠው፡ ሰው፡ የሚገባውን፡ አሳብ፡
አስብ፡ ዘንድ፡ ሰጠኝ።
፲፮፡ እኛ፡ ሁላችን፡ በጁ፡ ስለ፡ ተያዝን፡ ነገራችንም፡
ሁሉ፡ ሥራችንንም፡ ማወቅ፡ መረዳት፡ በጁ፡
ተይዟልና።
፲፯፡ ያለ፡ ሐሰት፡ ነዋሪ፡ የሚሆን፡ የውቀት፡ ነገርን፡
አስተማረኝ፡ ዓለም፡ ጸንቶ፡ የሚኖርበትን፡
ሥርዓት፡ አውቅ፡ ዘንድ። የጨረቃና፡ የፀሐ
ይን፡ የከዋክብትንም፡ ሥራ፡ አውቅ፡ ዘንድ።
፲፰፡ መጀመሪያውን፡ መጨረሻውን፡ የዘመኑን፡ መከ
ከል፡ የቀኑን፡ መለዋወጥ፡ የየጊዜውንም፡ መለ
ዋወጥ።
፲፱፡ የዘመኑንም፡ መለዋወጥ፡ የከዋክብትንም፡ አነ
ዋወር።
፳፡ የእንስሳንም፡ ጠባይ፡ የአራዊትንም፡ ብሕርይ።
የነፋሳትንም፡ ምሥጢር፡ የሰውንም፡ አሳብ።
እንጨቶችንም፡ ለይቶ፡ ማወቅ፡ የሥራቸው
ንም፡ ምሥጢር፡ አውቅ፡ ዘንድ፡ አስተማረኝ።
፳፩፡ ሥራውን፡ ሁሉ፡ የሚያስገኝ፡ እርሱ፡ ጥበቡን፡
አስተምሮኛልና፡ የተገለጸውንና፡ የተሠወረ
ውን፡ ሁሉ፡ አወቅሁ።
፳፪፡ የተመሰገነ፡ በልደት፡ የሠለጠነ፡ እውቀትን፡
የሚገልጥ፡ መንፈስ፡ ቅዱስ፡ በርሱ፡ ህልው፡
ነውና። እከሉ፡ አንድ፡ ሲሆን፡ በብዙ፡ ይከፈ
ላል፡ ረቂቅ፡ የሚሆን፡ አስተዳደሩም፡ ፈጣን፡
የሚሆን፡ ሲያስተምርም፡ ቃሉ፡ የሚያምር፡
አዋቂም፡ የሚሆን፡ ኃጢአት፡ የሌለበት፡ ድካ
ምም፡ የሌለበት፡ ቅድመ፡ ዓለም፡ የነበረ፡
ጥንት፡ የሌለው፡ ቸርነትን፡ የሚወድ፡ አዋቂ፡
የሚሆን፡ ልደር፡ ባለ፡ ጊዜ፡ የሚከለክለው፡
የሌለ።
በጎ፡ ነገርን፡ የሚያደርግ፡ ሰው፡ ወዳጅ፡ የሚ ፳፫፡
ሆን፡ ለጥበብ፡ ስምምዋ፡ የሚሆን፡ በውነት፡
አዋቂ፡ የሚሆን፡ ያለ፡ ግዳጅ፡ የሚሆን፡ ሁሉን፡
የሚችል፡ ሁሉን፡ የሚጐበኝ፡ ንጹሐት፡ በሆኑ፡
ረቂቆችና፡ ብልሆች፡ በሆኑ፡ ሰውነቶች፡ የሚ
ያድር።
የጥበብ፡ አስተዳደር፡ የማድጋውን፡ በጋን፡ ፳፬፡
የሚገለብጠውት፡ ይፈጥናልና፡ አድራ፡ የምታ
ነፃ፡ ስለ፡ ሆንች፡ በሁሉ፡ አድራ፡ ትኖራለች።
የእግዚአብሔር፡ ወልድ፡ የኃይሉ፡ መግለጫ፡ ፳፭፡
ናትና፡ ሁሉን፡ የያዘ፡ የጌትነቱም፡ መግለጫ፡
ናትና፡ መልኩ፡ የታወቀ፡ ምስጉን፡ ንጹሕ፡
የሚሆን፡ የኃይሉ፡ መግለጫ፡ ናትና። ስለዚህ፡
ነገር፡ ምንምን፡ ኃጢአት፡ የሚያገኛት፡ የለም።
የቀዳማዊ፡ አብ፡ ልጅ፡ መግለጫ፡ ናትና፡ ይህች፡ ፳፮፡
የማታልፍ፡ የእግዚአብሔርን፡ ሥራ፡ የምትገ
ልጥ፡ ናትና።
ቸርነቱንም፡ የምትገልጥ፡ ናትና፡ አንዲት፡ ፳፯፡
ስትሆን፡ ሁሉን፡ ማድረግ፡ ትችላለች። በቅ
ድምና፡ ሳለች፡ ሁሉን፡ ታድሳለች፡ ከንዱ፡
ትውልድ፡ ወደንዱ፡ ትውልድ፡ ወርዳ፡ በጻድቃ
ንች፡ ሰውነት፡ ታድራለች። ከጥበብ፡ ጋራ፡
ጸንቶ፡ ከሚኖር፡ ሰው፡ በቀር።
እግዚአብሔር፡ የሚወደው፡ የለምና፡ መምህ ፳፰፡
ራኖችና፡ የእግዚአብሔር፡ ወዳጆች፡ ታደርጋ
ቸዋለች።
ከፀሐይ፡ ይልቅ፡ ታበራለችና፡ ከከዋክብትም፡ ፳፱፡
ብርሃን፡ ሁሉ፡ ትበልጣለችና። ከብርሃን፡ ጋራ፡
በተመዘነች፡ ጊዜ፡ መንገዛላው፡ በሬቱ፡ ትገኛ
ለች።
ብርሃኑን፡ ሌሊት፡ ይለውጠዋልና፡ ጥበብን፡ ፴፡
ግን፡ ምንምን፡ ክፉ፡ ነገር፡ አይበረታባትምና።

ምዕራፍ፡ ፰።

ከዳርቻ፡ እስከ፡ ዳርቻ፡ ድረስ፡ ከጨለማ፡ ፩፡
ድና፡ ታበራለች፡ በቸርነቷም፡ ሁሉን፡ ትሠራ
ለች። ይህቺን፡ ጥበብን፡ ወደድኋት፡ ከሕፃንነ
ቷም፡ ጀምሬ፡ ፈለግኋት።
እኔም፡ እጮሐዳት፡ ዘንድ፡ ወደድሁ። ፪፡
የመዘመዷ፡ ቸርነት፡ ወደ፡ እግዚአብሔር፡ ያቀ ፫፡
ርባልና፡ ደግ፡ ግብሯን፡ የምወድ፡ ሆንኩ።
የእግዚአብሔርን፡ ምሥጢር፡ ለማወቅ፡ መክር፡ ፬፡
ናትና፡ ሁሉን፡ የሚገዛ፡ እርሱ፡ ወደዳት፡ ክፍ
ጥረቱም፡ ሁሉ፡ ትበልጣለች።
እርሷም፡ ከለች፡ ዘንድ፡ ብዕል፡ ናት፡ በዚህ፡ ፭፡
ዓለም፡ ገንዘብ፡ ባደረጓት፡ ሰዎች፡ ከሁሉ፡ ትመ
ረጣለች።
ሁሉን፡ የምታደርግ፡ ጥበብን፡ የሚበልጣት፡ ፮፡
ምንድነው፡ እውቀትም፡ ቢደረግ፡ በርሷ፡ ነው።
በዚህ፡ ዓለም፡ ካሉት፡ ከርሷ፡ የሚበልጥ፡ ፯፡
ብልህ፡ ማነው። እውነት፡ ነገርን፡ የወደደ፡

ሰውም ፡ ቢኖር ፡ በርሷ ፡ ነው ፡ ድካሟ ፡ ያማረ ፡
ነውና ፡ ጥበብና ፡ ንጽሕናን ፡ ጽንዕንና ፡ እውነ
ትን ፡ ደጋጎችንና ፡ ትሩፋትን ፡ ታስተምራለች ።
ከርሷ ፡ የሚሻልና ፡ የሚጠቅም ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡
ምንምን ፡ የለም ፡ የሰው ፡ ሕይወት ፡ ናት ።
፰ ፡ ደጋጎችንና ፡ ብዙ ፡ እውቀትን ፡ ያወቀ ፡ ሰው ፡
ቢኖር ፡ በርሷ ፡ ነው ። ያለፈውንም ፡ የሚመ
ጣውንም ፡ ያወቀ ፡ ሰው ፡ ቢኖር ፡ በሷ ፡ ነው ።
ፈጥኖ ፡ መተርጐምና ፡ የነገር ፡ መልስንም ፡ ቢያ
ውቅ ፡ በሷ ፡ ነው ። ተአምራትንና ፡ ምልክቱ
ንም ፡ አስቀድሞ ፡ ቢያውቅ ፡ የዘመኖችንና ፡ የሰዓ
ቶችንም ፡ መለዋወጥ ፡ ቢያውቅ ፡ በሷ ፡ ነው ።
፱ ፡ ለበጎ ፡ ነገር ፡ የምትገሥጽና ፡ የምትመክር ፡ ትካ
ዝንና ፡ ኃዘንን ፡ የምታስተው ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡
አውቄ ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ልትኖር ፡ እኔ ፡ እይዛት ፡
ዘንድ ፡ ወደድሁ ።
፲ ፡ እሷን ፡ ስለ ፡ ያዝኩ ፡ ሕፃን ፡ የምሆን ፡ እኔ ፡
በብዙ ፡ ሰዎች ፡ ዘንድ ፡ ምስጋናን ፡ በሊቃውን
ትም ፡ ዘንድ ፡ መከበርን ፡ አገኘሁ ።
፲፩ ፡ ለመፍረድ ፡ እንደበቴ ፡ የሰላ ፡ ልቡናዬ ፡ ነገር ፡
የበላ ፡ ሆነ ። በኃያላኑም ፡ ፊት ፡ ተደነቅሁ ።
፲፪ ፡ ዝም ፡ ስል ፡ ታግሠው ፡ ይጠብቁኝ ፡ ነበር ፡ ስና
ገርም ፡ ይሰሙኝ ፡ ነበር ። መናገርም ፡ ባበዛ ፡
አፋቸውን ፡ በጃቸው ፡ ይዘው ፡ ይቀመጡ ፡ ነበር።
፲፫ ፡ ስለሷ ፡ አለመሞትን ፡ አገኘሁ ፡ ከኔ ፡ በኋላም ፡
በሚነሡም ፡ ሰዎች ፡ ለዘለዓለም ፡ መታሰቢያን ፡
ተውኩ ።
፲፬ ፡ ሕዝቡን ፡ እሠራራ ፡ ነበር ፡ አሕዛብም ፡ ይገዙ
ልኝ ፡ ነበር ።
፲፭ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ያሉ ፡ የሚያስደነግጡ ፡ መኳን
ንት ፡ ዝናዬን ፡ ሰምተው ፡ ይፈሩኝ ፡ ነበር ። በሸ
ንጎ ፡ ደግ ፡ ሆኜ ፡ እታይ ፡ ነበር ፡ በጦብም ፡ ጊዜ ፡
የጸናሁ ፡ ሁኜ ፡ እታይ ፡ ነበር ።
፲፮ ፡ ከሷ ፡ ጋራ ፡ መኖር ፡ ኃዘን ፡ የለበትምና ፡ ወደ
ሷም ፡ ኃዘን ፡ አይቀርብምና ፡ ከዘመቻ ፡ ወደ ፡
ቤቴ ፡ በተመለስኩም ፡ ጊዜ ፡ በርሷ ፡ አርፍ ፡ ነበር።
ከፍጹም ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ በቀር ፡ ኃዘን ፡ ወደ
ርሷ ፡ አይቀርብምና ።
፲፯ ፡ ይህንን ፡ በአእምሮዬ ፡ ሳወጣ ፡ ሳወርድ ፡ ኖርኩ ።
በልቡናዬም ፡ በሷ ፡ እታገላለሁ ፡ የጥበብ ፡
ተዘምዶዋ ፡ ያለመሞት ፡ ነውና ፡ ከኃጢአት ፡
መንጻት ፡ እንዳይቻለኝ ፡ አውቄ ፡ በሷ ፡ በል
ቡናዬ ፡ እተጋለሁ ።
፲፰ ፡ እርሷንም ፡ በመውደድ ፡ በጎ ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡
አለና ፡ በጁ ፡ ሥራም ፡ የማያልቅ ፡ ብዕል ፡ አለና ፡
ምሥጢሯን ፡ በመመልከት ፡ የውቀት ፡ ትእም
ርት ፡ ያገኛልና ፡ ከሷም ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ በመ
ሆን ፡ የሚያስመካ ፡ ነገር ፡ ይገኛልና ፡ ሙሽራ ፡
ልትሆነኝ ፡ አገባት ፡ ዘንድ ፡ ስፈልጋት ፡ አገሩን ፡
ሁሉ ፡ ዞርኩ ።
፲፱ ፡ አዋቂ ፡ ልጅ ፡ የምሆን ፡ እኔ ፡ ዞርኩ ፡ ሰውነ
ቴም ፡ በጎ ፡ ሆነችልኝ ።
፳ ፡ ደግ ፡ ነኝና ፡ ንጹሕ ፡ ወደ ፡ ሆነ ፡ ሥጋዋ ፡ ገባሁ ።
፳፩ ፡ እግዚአብሔር ፡ እሷን ፡ ካልሰጠኝ ፡ ከኃጢአት ፡
መንጻት ፡ እንዳይቻለኝ ፡ በወቅሁ ፡ ጊዜ ። ምክር ፡
ከጥበብ ፡ የነተሣ ፡ ሆነ ፡ ይህቺም ፡ ስጦታ ፡ ለማንም ፡
ለማንም ፡ እንደሆነች ፡ አውቅ ፡ ዘንድ ፡ ፈጽሜ ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለመንኩ ።

ምዕራፍ ፡ ፱ ።

በፍጹም ፡ ልቡናዬ ፡ እንዲህ ፡ አልኩ ፡ ያቤቴ ፡ ፩
ፈጣሪ ፡ የቸርነት ፡ ባለቤት ።
በቃልህ ፡ ዓለሙን ፡ ሁሉ ፡ የፈጠርክ ፡ ባንተ ፡ ፪
ትእዛዝ ፡ የተፈጠረ ፡ አዳም ፡ በጥበብህ ፡ ሰውን ፡
እንዲገዛ ፡ ያደረግኸው ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ እንዲ
ኖር ፡ በቸርነቱ ፡ ዓለምን ፡ እንዲሠራ ።
በውነት ፡ በቀና ፡ ልቡና ፡ ፍርድን ፡ እንዲፈርድ ፡ ፫
ያደረግኸው ።
በኪሩቤል ፡ አድራ ፡ የምትኖር ፡ ጥበብን ፡ ስጠኝ። ፬
ከባሮችህ ፡ መካከል ፡ አትለየኝ ፡ የሴት ፡ ባሪያህ ፡ ፭
ልጅ ፡ ባሪያህ ፡ ነኝና ፡ ኃይል ፡ የደከመ ፡ ሰው ፡
የምሆን ፡ ዘመኔ ፡ ያነሰኝ ፡ ሕጉን ፡ ፍርዱን ፡ ለማ
ወቅ ፡ ትሑት ፡ አእምሮ ፡ የምሆን ፡ እኔ ፡ የሴት ፡
ባሪያህ ፡ ልጅ ፡ ባሪያህ ፡ ነኝና ፡ ከባሮችህ ፡
አትለየኝ ።
ከሰው ፡ ልጆችም ፡ ፍጹም ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ ቢኖር ፡ ፮
በሷ ፡ ነው ፡ ባንተ ፡ ዘንድ ፡ የምትገኝ ፡ ጥበብ ፡
ከሱ ፡ ከራቀች ፡ እርሱ ፡ እንደ ፡ ኢምንት ፡
በሆነ ፡ ነበርና ።
አንተ ፡ ለወገኖቼ ፡ ንጉሥ ፡ አድርገህ ፡ መረጥ ፡ ፯
ኸኝ ፡ ሴሴት ፡ ልጆችህና ፡ ለወንዶች ፡ ልጆች
ህም ፡ ገዢ ፡ አደረግኸኝ ።
በመመስገኛህ ፡ በታ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ይሠራ ፡ ፰
በማረፊያህም ፡ አገር ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ ባዘጋ
ጀኸው ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ተብለህ ፡
በምትመሰገንበት ፡ ጽርሐ ፡ አርያም ፡ አምሳል ፡
መሠዊያህ ፡ ይሠራ ፡ አልኩ ።
ካንተ ፡ ጋራ ፡ ያለች ፡ ጥበብ ፡ ሥራህን ፡ ታውቅ ፡ ፱
ነበር ፡ ዓለምንም ፡ በፈጠርክ ፡ ጊዜ ፡ ነበረች ፡
በፊትህ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝህ ፡ ምንም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
ለትእዛዝህም ፡ የቀናው ፡ ምንም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
ትረዳ ፡ ነበር ።
ተነሥታ ፡ ትመጣ ፡ ዘንድ ፡ ከከበሩ ፡ ሰማዮች ፡ ፲
ከጌትነትህ ፡ ዙፋን ፡ ወደኔ ፡ ላካት ። ከኔ ፡ ጋራ ፡
ትኖር ፡ ትደክም ፡ ዘንድ ፡ ደስ ፡ ለሚያሰኝህ ፡
ምንምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ልወቅ ።
አንተ ፡ የምታውቀውን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ታውቃ ፡ ፲፩
ለችና ።
ንጹሕ ፡ አድርጋ ፡ ወደ ፡ ሥራዎች ፡ ሁሉ ፡ ትም ፡ ፲፪
ራኝ ፡ በክብሯ ፡ ትጠብቀኝ ፡ ሥራዬ ፡ ሁሉ ፡ የተ
ወደደ ፡ ይሁን ፡ ወገኖችህን ፡ በውነት ፡ ልግዛ ፡
ላባቶቼ ፡ ዙፋኖችም ፡ የተዘጋጀሁ ፡ ልሁን ።
የእግዚአብሔርን ፡ ምክር ፡ የሚያውቅ ፡ ሰው ፡ ፲፫
ማነው ።
የሚቾች ፡ አሳባቸው ፡ ፈራሽ ፡ ነውና ፡ አሳባቸ ፡ ፲፬
ውም ፡ ጉግጉፅ ፡ ነውና ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚ
ወደውን ፡ አስበ ፡ የሚያውቅ ፡ ማነው ።
የሚፈርስ ፡ ሥጋ ፡ ነፍስን ፡ ያሸንፋታል ፡ ያፈዘ ፡ ፲፭

ታልና ፡ ምድራዊ ፡ ሥጋ ፡ ልብን ፡ ያደንቍራ
ታልና ።
፲፮፤ በብዙ ፡ ትጋት ፡ በብዙ ፡ ግዳጅ ፡ በጭንቅ ፡ ብን
መረምር፡ በምድር ፡ የሚሠራውን ፡ ሥራ ፡ እና
ገኛለን ፡ በእጃችን ፡ የምንዳስሰውን ፡ ሥራ ፡ በድ
ካም ፡ እናገኛለን ። በሰማይ ፡ ያለውን ፡ ሥራ ፡
ግን ፡ ማን ፡ መረመረው ፡ ምክርህንስ ፡ ማን ፡
አወቀ ።
፲፯፤ አንተ ፡ ጥበብን ፡ ያሰጠኸው ፡ ካልሆነ ፡ የከበረ፡
የሆነ፡ መንፈስ፡ቅዱስንም፡ ወደሱ፡ የላክህለት፡
ካልሆነ፡ ምክርህን ፡ ማን ፡ አወቀ ።
፲፰፤፲፱፤ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ያሉ ፡ ሰዎች ፡ ሥራቸው ፡ ስለ
ዚች ፡ ቀናባቸው ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝህም ፡ ነገር ፡
ሰዎች ፡ በጥበብ ፡ አወቁ ፡ በዚችም ፡ ዳኑ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩፤ ይቺ ፡ ጥበብ ፡ ብቻውን ፡ አስቀድሞ ። የተፈ
ጠረ ፡ አዳምን ፡ ጠበቀችው ። ከተፈጠረም ፡
በኋላ ፡ እንደ ፡ አደራ ፡ ዕቃ ፡ ጠበቀችው ፡ ከራሱ፡
ኃጢአትም ፡ አዳነችው ።
፪፤ ፈጽሞ ፡ ይገዛ ፡ ዘንድ ፡ ኃይልንም ፡ ሰጠችው ።
፫፤ በደለኛ ፡ የሚሆን ፡ ሰው ፡ ከሷ ፡ በራቀ ፡ ጊዜ ፡
ወንድሞቻቸውን ፡ ከሚገድሉ ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡
በእግዚአብሔር ፡ መዓት ፡ ጠፋ ።
፬፤ ዳግመኛ ፡ ምድር ፡ በማየ ፡ አይህ ፡ በጠፋች ፡
ጊዜ ፡ ጥበብ ፡ ኖኅን ፡ አዳነችው ፡ በተናቀ ፡ እን
ጨት ፡ ዕቃም ፡ አሻገረችው ።
፭፤ አሕዛብ ፡ ወደ ፡ ጥመትና ፡ ወደ ፡ ክፋት ፡ ቅመም ፡
ተጨልጠው ፡ በሔዱ ፡ ጊዜ ፡ አብርሃምን ፡ አመ
ለከተችው ፡ ያለነውርና ፡ ያለነቀፋም ፡ ለእግ
ዚአብሔር ፡ ቢገዛ ፡ ጠበቀችው ። በቸርነቱ
የጸና ፡ ልጁንም ፡ ጠበቀች ።
፮፤ ከሚጠፉ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ከሚዘነጉ ፡ ሰዎች ፡
ለይታ ፡ ይቺ ፡ ጥበብ ፡ ሎጥን ፡ አዳነች ፡ በም
ስቱ ፡ አገሮች ፡ ላይ ፡ እሳት ፡ በወረደ ፡ ጊዜ ፡ በመ
ሸሽ ፡ አዳነችው ።
፯፤ ለክፋታቸው ፡ ምስክር ፡ ልትሆን ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡
ድረስ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሆና ፡ ስትጤስ ፡ አለች ፡
ተክሎቿም ፡ በጊዜዋ ፡ ጊዜ ፡ ቢያፈሩ ፡ ፍጹ
ማን ፡ ያልሆኑ ፡ ናቸው ። ያላመነች ፡ ሰውነትም ፡
መታሰቢያ ፡ ሆና ፡ የሚታይ ፡ የጨው ፡ ደንጊያ ፡
ሆና ፡ ቆመች ። (ብእሲተ ፡ ሎጥ)
፰፤ እለዚህ ፡ ትእዛዙን ፡ የተላለፉ ፡ ናቸውና ፡ የበ
ደሉትን ፡ በደል ፡ መሠወር ፡ እንዳልተቻላቸው፡
መጠን ፡ ለስንፍናቸው ፡ መታሰቢያን ፡ በዚህ፡
ዓለም ፡ ተዉ ፡ እንጂ ፡ እንደ ፡ ሰብአ ፡ ትክት ፡
የደረሰባቸውን ፡ መዓት ፡ በማወቅ ፡ እንደዚያ ፡
የጠፉ ፡ አይደለም ።
፱፤ ጥበብስ ፡ የሚያገለግሏትን ፡ ሰዎች ፡ ከድካም ፡
አዳነች ።
፲፤ ይህች ፡ ከወንድሙ ፡ ቍጣ ፡ የተነሣ ፡ የሸሸ ፡
ደግ ፡ ሰው ፡ ያዕቆብን ፡ ወደ ፡ ቀና ፡ መንገድ ፡ መራ
ችው ። የእግዚአብሔርንም ፡ መንግሥት ፡ አሳ
የችው ፡ (ሰዋስወ ፡ ወርቅ ፡) መላእክትንም ፡
ማወቅ ፡ ሰጠችው ፡ ከድካሙ ፡ የተነሣ ፡ ብዕሉን ፡
አበዛችለት ።
ከሚቀሙት ፡ ከሚበረታቱበትም ፡ ሰዎች ፡ ፲፩፤
ጠበቃ ፡ ሆና ፡ ቆመችለት ።
ረዳችው ፡ ጠበቀችው ፡ ከጠላቶቹም ፡ እንደ ፡ ፲፪፤
አደራ ፡ ዕቃ ፡ ጠበቀችው ፡ ከከበቡት ፡ ሰዎ
ችም ፡ አዳነችው ። ለእግዚአብሔር ፡ በበጎ ፡
መገዛት ፡ ከሁሉ ፡ እንዲጸና ፡ ያውቅ ፡ ዘንድ ፡
ጽኑ ፡ ገድልን ፡ በሰጠችው ፡ ጊዜ ፡ ስም ፡ አወ
ጣችለት ።
ይህቺ ፡ ጥበብ ፡ ወደ ፡ ግብፅ ፡ አብራው ፡ ወረ ፲፫፤
ደች ፡ እንጂ ፡ በተሸጠ ፡ ጊዜ ፡ ደግ ፡ ሰው ፡ ዮሴ
ፍን ፡ አልተለየችውም ፡ ከኃጢአትም ፡ አዳነ
ችው ።
በተበረታቱበትም ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ ግዛትንና ፡ የመ ፲፬፤
ንግሥትን ፡ ሹመት ፡ እስክታመጣለት ፡ ድረስ ፡
በታሠረበትም ፡ አልተለየችው ። የናቁትና ፡
ከብላይ ፡ በሬያ ፡ ያሉት ፡ የወንድሞቹንም ፡ ሐሰ
ታቸውን ፡ ገለጠችባቸው ። የዘለዓለምንም ፡
ሹመት ፡ ሰጠችው ።
ይህቺም ፡ ጥበብ ፡ ደግ ፡ ወገን ፡ እስራኤልን ፡ ፲፭፤፲፮፤
አዳነች ፡ በእግዚአብሔር ፡ ባሪያ ፡ በሙሴ ፡ ሰው
ነት ፡ አድራ ፡ ከሚያስጨንቁ ፡ ከአሕዛብ ፡ ነውር ፡
ነቀፋ ፡ የሌለው ፡ ልጅን ፡ አዳነች ፡ (እስራኤልን፤)
በተአምራትና ፡ በአምልክት ፡ ብዙ ፡ ነገሥታ
ትን ፡ ተቃወመች ።
የድካማቸውንም ፡ ዋጋ ፡ ሰጠቻቸው ፡ የተደነቀ፡ ፲፯፤
መንገድንም ፡ መራቻቸው ፡ በቀን ፡ ጥላ ፡ ሆነቻ
ቸው ፡ በሌሊትም ፡ ስለከዋክብት ፡ ብርሃን ፡
ፋንታ ፡ ብርሃን ፡ ሆና ፡ አበራችላቸው ።
የተፈራ ፡ ባሕርንም ፡ አሻገረቻቸው ፡ በሰፊ ፡ ፲፰፤
ውኃ ፡ መካከልም ፡ አሳለፈቻቸው ።
ጠላቶቻቸውን ፡ ግን ፡ አሰጠመች ፤ እስራኤልን ፡ ፲፱፤
ግን ፡ ከጥልቅ ፡ ባሕር ፡ አወጣቻቸው ።
ስለዚህ ፡ ነገር ፡ እስራኤል ፡ እግዚአብሔርን ፡ ፳፤
የዘነጉ ፡ ግብፃውያንን ፡ማረኩ ። አቤቱ ፡ የከበረ ፡
ስምህንም ፡ አመሰገኑ ።
ጥበብ ፡ የዲዳዎችን ፡ አፍ ፡ ገልጣለችና ፡ የሕፃና ፳፩፤
ቶችንም ፡ አንደበት ፡ ቀንቶ ፡ የሚናገር ፡ አድ
ርጋለችና ፡ አርበኛ ፡ አሽናፊ ፡ የምትሆን ፡ ሥል
ጣንህንም ፡ አንድነት ፡ አመሰገኑ ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፩ ።

ክቡር ፡ በሚሆን ፡ በነቢዩ ፡ ሥልጣን ፡ ሥራ ፩፤
ቸውን ፡ እርሱ ፡ አቅንቷልና ፡ ማንምማን ፡ ወዳ
ልኖረበት ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሄደው ፡ ኖሩ ።
በሰው ፡ ጫማ ፡ ባልተረገጠች ፡ በታም ፡ የድን ፪፤
ኳኖቻቸውን ፡ ከስማ ፡ ተከሉ ።
አርበኞችን ፡ ተቀዋወሟቸው ፡ ጠላቶችንም ፡ ፫፤
ተበቀሏቸው ።
ተጠምተው ፡ ለመኑህ ፡ ከቡልጨት ፡ ደንጊያ ፡ ፬፤
ውኃ ፡ ተሰጣቸው ።
ከጽኑ ፡ ድንጊያም ፡ ጽማቸውን ፡ ሊያርቅላቸው ፡ ፭፤
ውኃ ፡ ተሰጣቸው ። ጠላቶቻቸው ፡ ግብፃውያን ፡

ለዚህ ፡ ሥራ ፡ ተቀጡ ፡ ጠፉ ።
፭፤ በመከራው ፡ ተይዘው ፡ በተጨነቁ ፡ ጊዜ ፡ ለነ
ዚህ ፡ ግን ፡ በዚህ ፡ አምሳል ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ አደረግ
ህላቸው ።
፮፤ ስለማይገድል ፡ እኒህ ፡ ግብፃውያን ፡ በሞቱት ፡
ልጆች ፡ ደም ፡ ስለ ፡ አደፈረሱ ፡ ወንዝ ፡ ምንጭ ፡
ፈንታ ።
፯፤ ሕፃናትን ፡ ለምትገድል ፡ ለግብፅ ፡ ዘለፋ ፡ ሊሆ
ንበት ፡ ነግ ፡ ሠልስት ፡ ያለማለት ፡ ፈጥነህ ፡ ያፈ
ሰስከውን ፡ ብዙ ፡ ውኃ ፡ ሰጠኻቸው ።
፰፤ ከተጠሙ ፡ በኋላ ፡ በተፈታተኑህ ፡ ጊዜ ፡ እንደ
ዚሁ ፡ በሚቃወሙህ ፡ በእስራኤል ፡ ፈረድህ ።
፱፤ እነሱ ፡ ግን ፡ በምሕረትህ ፡ ዳኑ ፡ ሕግህን ፡ የዘነጉ ፡
እስራኤል ፡ በተፈረደባቸው ፡ ጊዜ ፡ ግብፃው
ያን ፡ በመዓት ፡ እንደ ፡ ተቄጡ ፡ አወቁ ።
፲፤ እነዚህን ፡ እስራኤልን ፡ እንደሚቀጣ ፡ አባት ፡
መከርኻቸው ።
፲፩፤ እኒህን ፡ ግብፃውያንን ፡ ግን ፡ ርኅራኄ ፡ እንደሌ
ለው ፡ ንጉሥ ፡ ተከትለህ ፡ በረበርህ ፡ በዚህ ፡ ርኅ
ራኄ ፡ በሌለው ፡ ንጉሥ ፡ አምሳል ፡ አጠፋኻ
ቸው ።
፲፪፤ እጥፍ ፡ ኀዘን ፡ አግኝታቸዋለችና ፡ በሀገራቸ
ውም ፡ ሳሉ ፡ በሀገራቸውም ፡ ሳይኖሩ ፡ ግብፃው
ያንን ፡ አሳዘንሃቸው ። ክፉ ፡ ፈርዖን ፡ አውቆት ፡
ያለፈ ፡ ዘጠኙ ፡ መቅሠፍት ፡ ሞተ ፡ በኋርን ፡
የሚያሳስብ ፡ ነበር ።
፲፫፤ በመከራቸው ፡ ለእስራኤል ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ እንዳ
ደረገላቸው ፡ በሰሙ ፡ ጊዜ ፡ እነሱም ፡ ከእግዚ
አብሔር ፡ የተገኘ ፡ ደስታ ፡ አደረጉት ።
፲፬፤ ዳግመኛም ፡ በክፋታቸው ፡ ቀድሞ ፡ በባሕር ፡
የጣሉት ፡ ሙሴን ፡ ምድያም ፡ ሄዶ ፡ አጡት ፡
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ዋዘ ፡ በሚሆን ፡ በትንኝ ፡ ጠፉ ።
የዘጠኙ ፡ መቅሠፍት ፡ ፍጻሜ ፡ ከሚሆን ፡ ከሞተ ፡
በኵር ፡ የተነሣ ፡ ግብፃውያን ፡ አደነቁ ፡ ጻድቃን ፡
እስራኤል ፡ እንደ ፡ ተጠማ ፡ ግብፃውያን ፡ የተ
ጠሙ ፡ አይደሉም ።
፲፭፤ አእምሮ ፡ ስለሌላት ፡ ስለ ፡ ልቡናቸው ፡ ክፋት ፡
በዚች ፡ በሳቱ ፡ ጊዜ ፡ የተናቀ ፡ ከንቱ ፡ የሚሆን ፡
ስጦታ ፡ የማይናገር ፡ እንስሳን ፡ አምልከዋልና ።
፲፮፤ ሰው ፡ በበደለበት ፡ ሥራ ፡ እንዲፈረድበት ፡
ያውቁ ፡ ዘንድ ፡ የማይናገር ፡ ብዙ ፡ እንስሳን ፡
አመጣህባቸው ።
፲፯፤ ሁሉን ፡ ለሚችል ፡ ለሥልጣንህ ፡ አይሳነውምና ።
ቍጡ ፡ የሆኑ ፡ አንበሶችንና ፡ ብዙ ፡ ድቦችን ፡
ታመጣባቸው ፡ ዘንድ ፡ እምኀበ ፡ አልበ ፡ ዓለ
ምን ፡ ለፈጠረች ፡ ለሥልጣንህ ፡ አይሳናትምና ።
፲፰፤ ይህም ፡ ባይሆን ፡ ድንገት ፡ የተፈጠሩ ፡ የማይ
ታወቁ ፡ የሚያላልቡና ፡ የሚፋጅ ፡ እሳትን ፡
የሚተነፍሱ ፡ ይህም ፡ ባይሆን ፡ የሚከረፋ ፡
የጢስ ፡ መዓዛን ፡ የሚተነፍሱ ፡ ይህም ፡ ባይሆን ፡
ክፉ ፡ ከሚሆን ፡ ያይናቸው ፡ የብረት ፡ ፍንጣሪ ፡
የመሰለ ፡ በግ ፡ በግ ፡ የሚያደርጉ ፡ መዓትን ፡
የተመሉ ፡ አውሬዎችን ፡ ታመጣ ፡ ዘንድ ፡ አይ
ሳናትምና ፡ ሳይሳናት ።
መልካቸው ፡ አስፈሪርቶ ፡ ባጠፋቸው ፡ ነበር ፡ ፲፱፤
እንጂ ፡ ያጠፋቸው ፡ ዘንድ ፡ የሚችል ፡ ክፋታ
ቸው ፡ መቻያነታቸው ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፡ መዓ
ትን ፡ የተመሉ ፡ አውሬዎችን ፡ ታመጣ ፡ ዘንድ ፡
አይሳናትም ፡ ሳይሳናት ።
በቃልህ ፡ በሞት ፡ አሰወጥተህ ፡ ስትሰዳቸው ፡ ፳፤
ሥልጣንህን ፡ በምትገልጽበት ፡ ኃይልም ፡ ስታ
ጠፋቸው ፡ ያለዚህም ፡ በንድ ፡ ምልክት ፡ ይጠፉ ፡
ዘንድ ፡ በተገባቸው ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ እንዲህ ፡
እንዲህ ፡ ለምታደርግ ፡ ለሥልጣንህ ፡ አይሳና
ትምና ፡ ሳይሳናት ።
ሁልጊዜ ፡ የከሃሊነትህ ፡ ገናንነት ፡ ካንተ ፡ ጋር ፡ ፳፩፤
አለና ፡ ነገር ፡ ንግ ፡ ሁሉን ፡ በልክ ፡ በመጠን ፡
ሠራህ ፡ በፊትህ ፡ ዓለሙ ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ሚዛን ፡
እንደበት ፡ ውልብልቢት ፡ ማለዳ ፡ በምድር ፡ ላይ ።
እንደ ፡ ወረደች ፡ እንደ ፡ ጠል ፡ ጠብታም ፡ በፊ ፡ ፳፪፤
ትህ ፡ የተናቀ ፡ ነውና ፡ የጸናች ፡ ሥልጣንህን ፡
የሚቃወማት ፡ ማነው ።
አንተ ፡ ሁሉን ፡ የምትችል ፡ ነህና ፡ ሁሉን ፡ ይቅር ፡ ፳፫፤
ትላለህ ፡ ለንስሐ ፡ እያቆየኸው ፡ የሰውንም ፡ ኃጢ
አት ፡ ቸል ፡ ትላለህ ።
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ያሉትን ፡ ሰዎች ፡ ሁሉን ፡ ትወ ፡ ፳፬፤
ዳለህ ፡ ጠልተህ ፡ የፈጠርከው ፡ የለምና ፡ ከፈጠ
ርኸው ፡ ፍጥረት ፡ ምንም ፡ ምን ፡ የምትንቀው ፡
የለም ።
አንተ ፡ ከጠላኸውማ ፡ በፊትህ ፡ እንዴት ፡ በጸና ፡ ፳፭፤
ነበር ። ከጠላኸው ፡ አንተ ፡ ካልወደድኸውስ ፡
ምንምን ፡ ባልፈጠርኸውም ፡ ነበር ። አንተ ፡
ወደህ ፡ ያልፈጠርኸው ፡ ካልሆነ ፡ እንዴት ፡ በተ
ጠበቀ ፡ ነበር ።
ለፍጥረቱም ፡ ሁሉ ፡ ትራራለህ ፡ ይቅር ፡ ትላለህ ። ፳፮፤

## ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

ሰው ፡ ወዳጅ ፡ የምትሆን ፡ አቤቱ ፡ ጥበብ ፡ ፩፤
ያንተ ፡ ገንዘብ ፡ ናትና ። ጥፋት ፡ የሌለበት ፡ ሕይ
ወትህ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ በዓለሙ ፡ ሁሉ ፡
አለና ።
ስለዚህ ፡ ነገር ፡ በኃጢአት ፡ የተሰነካከሉትን ፡ ፪፤
ሰዎች ፡ ለፍርድ ፡ እንዲመች ፡ ጥቂት ፡ ጥቂት ፡
እያልክ ፡ ትዘልፋቸዋለህ ፡ ከክፋታቸው ፡ ርቀው ፡
ኃጢአታቸውን ፡ በተረዱት ፡ ጊዜ ፡ አቤቱ ፡ ያም
ኑብህ ፡ ዘንድ ፡ የበደሉትን ፡ በደል ፡ እያሳሰ
ብክ ፡ ትገሥጻቸዋለህ ።
የተጠላ ፡ የሚሆን ፡ ስር ፡ የመማሳቸውን ፡ ቅጠል ፡ ፫፤ ፬፤
የመበጠሳቸውን ፡ ሥራ ፡ ጠልተህ ፡ ከውነት ፡
የራቀ ፡ በዓላቸውንም ፡ ጠልተህ ።
ያለርኅራኄ ፡ ልጆቻቸውን ፡ መግደላቸውንም ፡ ፭፤
ጠልተህ ። የሰዎች ፡ ሆድ ፡ ዕቃቸውን ፡ እሳት ፡
ሊበላው ፡ ማሰናበታቸውንም ፡ ጠልተህ ፡ በከነ
ዓን ፡ የሚኖሩ ፡ የቀደሙ ፡ የሰብእ ፡ ከነዓንን ፡
ሥራ ፡ ጠልተህ ፡ የጌትነትህን ፡ ምሥጢር ፡
ማወቅ ፡ ከልቡናቸው ፡ ርቋልና ።
ሥጋቸውን ፡ ማቃጠላቸውን ፡ ደማቸውን ፡ ማፍ ፡ ፮፤
ሰሳቸውን ፡ ጠልተህ ፡ ከማንም ፡ ከማንም ፡

ረዓት ፡ የሌላት ፡ ሰውነትን ፡ ይገድላሉና ፡ ይህ
ንን ፡ ጠልተህ ።
፯፤ የእግዚአብሔር ፡ ልጆች ፡ እስራኤል ፡ ከገሩ ፡
ሁሉ ፡ ባንተ ፡ ዘንድ ፡ የከበረች ፡ በነርሱ ፡ የም
ትገባ ፡ ከነዓንን ፡ ይይዙ ፡ ዘንድ ፡ በባዮቻችን ፡
ሥልጣን ፡ ታጠፋቸው ፡ ዘንድ ፡ ወደህልና ።
፰፤ ነገር ፡ ግን ፡ ሌላውን ፡ ሰው ፡ ይቅር ፡ እንድትል ፡
እነርሱንም ፡ ይቅር ፡ አልኻቸው ። እነርሱን ፡
ጥቂት ፡ ጥቂት ፡ እያሉ ፡ ሊያጠፉ ፡ ከወገኖችህ ፡
አስቀድሞ ፡ የትንኝ ፡ ወራሪ ፡ በላክህ ፡ ጊዜ ፡
ነገር ፡ ግን ፡ ሌላውን ፡ ይቅር ፡ እንድትል ፡ ይቅር ፡
አልክ ።
፱፤ ይህም ፡ ባይሆን ፡ በየወገኖቻቸው ፡ ይማርኳ
ቸው ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የዘነጉ ፡ የከነ
ዓንን ፡ ሰዎች ፡ በድኃጎች ፡ በእስራኤል ፡ እጅ ፡
ትጥላቸው ፡ ዘንድ ፡ አይሳንህም ፡ ነበርና ፡ ሳይ
ሳንህ ፡ ይህም ፡ ባይሆን ፡ ለክፉዎች ፡ አውሬ
ዎች ፡ ትሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ አይሳንህም ፡ ነበርና ፡
ሳይሳንህ ፡ ይህም ፡ ባይሆን ፡ ባንድ ፡ ቃል ፡ አገ
ዘህ ፡ ታጠፋቸው ፡ ዘንድ ፡ አይሳንህም ፡ ነበርና ፡
ሳይሳንህ ።
፲፤ ለነዚህ ፡ የንስሐ ፡ ዘመን ፡ ሰጥተህ ፡ ይህ ፡ ጥፋታ
ቸው ፡ በጥቂት ፡ በጥቂት ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ፈር
ደህ ፡ ይህንንም ፡ ማድረግህ ፡ አነዋወራቸው ፡
ክፉ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ክፋታቸውም ፡ እጅግ ፡ ብዙ ፡
እንደ ፡ ሆነ ።
፲፩፤ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ የተረገሙ ፡ ልጆች ፡ ናቸውና ፡
ልቡናቸውም ፡ ለዘለዓለሙ ፡ የማይመለስ ፡
እንደ ፡ ሆነ ፡ ሳታውቅ ፡ አይደለም ፡ ለበደሉበት ፡
ኃጢአታቸው ፡ መጥዕለ ፡ ንስሐ ፡ የምትሰጣ
ቸው ፡ ማንንም ፡ አፍረህ ፡ አይደለም ። ለምን ፡
እንዲህ ፡ አደረግህ ፡ የሚልህ ፡ ማነው ፡ ፍርድ
ህንስ ፡ የሚቃወመው ፡ ማነው ።
፲፪፤ ነገር ፡ ሠርቶ ፡ የሚያጣላህ ፡ አንተ ፡ የፈጠርኻ
ቸው ፡ አሕዛብስ ፡ ስለ ፡ ጠፉ ፡ የሚመራመርህ ፡
ማነው ።
፲፫፤ የፈረድህ ፡ በግፍ ፡ እንዳይደለ ፡ ትገልጥ ፡ ዘንድ ፡
ስለ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ የሚያስብ ፡ ካንተ ፡ በቀር ፡
ሌላ ፡ ፈጣሪ ፡ የለምና ፡ ስለ ፡ በደለኞች ፡ ሰዎች ፡
ለመከራከር ፡ ወደ ፡ አንተ ፡ የሚደርስ ፡ ዳኛ ፡
ማነው ።
፲፬፤ አንተ ፡ ሁሉን ፡ በውነት ፡ የምታዘጋጅ ፡ እውነ
ተኛ ፡ ነህና ፡ ስለ ፡ ፈረድክባቸው ፡ ሰዎች ፡ ሕያ
ማህ ።
፲፭፤ ንጉሥም ፡ ቢሆን ፡ ዳኛም ፡ ቢሆን ፡ ሹምም ፡
ቢሆን ፡ ከንተ ፡ ጋራ ፡ በጠብ ፡ ለመተያየት ፡ አይ
ችልም ። ትፈርድ ፡ ዘንድ ፡ ከክሀሊነትህ ፡ ጽድቅ
ነህ ፡ ለመፍረድ ፡ የማይገባ ፡ ልዩ ፡ ሥራን ፡ አደ
ረግህ ።
፲፮፤ ከሀሊነትህ ፡ የቸርነት ፡ መጀመሪያ ፡ ነውና ፡
ሁሉን ፡ መፍጠርህ ፡ ሁሉን ፡ መግዛትህ ፡ ሁሉን ፡
ይቅር ፡ እንድትል ፡ ያደርግሃል ።
፲፯፤ የከሀሊነትህን ፡ ጭራሽ ፡ ለማያውቅ ፡ በፈርዖን ፡
ኃይልህን ፡ ገልጠሃልና ፡ በማያምኑ ፡ በግብፃው
ያንም ፡ ገልጠኻልና ፡ በመደፋፈራቸው ፡ ምክ
ንያት ፡ ትዘልፋቸዋለህ ።
አንተ ፡ በየዋህነት ፡ የምትፈርድ ፡ አዋቂ ፡ ዳኛ ፡ ፲፰፤
ስትሆን ፡ ባንተ ፡ ዘንድ ፡ ከሀሊነት ፡ አለና ፡
መቼም ፡ መቼ ፡ ልትፈርድብን ፡ ወደህ ፡ ከብዙ ፡
ቸርነት ፡ ጋራ ፡ ታኖረናለህ ።
ርኅሩኅ ፡ ሰው ፡ ወዳጅ ፡ እስራኤል ፡ የተወደ ፲፱፤
ደን ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ በእንደዚህ ፡ ያለ ፡ ሥራ ፡
ወገኖችህ ፡ እስራኤልን ፡ ይቅር ፡ አልክ ። ለል
ጆችህ ፡ ለእስራኤል ፡ በጎ ፡ አለኝታ ፡ አደረግህ ።
አንተ ፡ ለበደለኛ ፡ ንስሐን ፡ ትሰጣለህና ፡ ልጆ
ችህ ፡ እስራኤልን ፡ ተናገርኻቸው ።
ለሞት ፡ የሚገቡ ፡ እኒህ ፡ የልጆችህ ፡ ጠላቶች ፡ ፳፤
ክሉ ፡ ዘንድ ፡ በእንዲህ ፡ ያለ ፡ ትዕግሥት ፡
የፈረድህ ፡ ዘመንን ፡ የሰጠኻቸው ፡ ከክፉ ፡ ነገር ፡
ይድኑበት ፡ ዘንድ ፡ ፍኖተ ፡ ንስሐንም ፡ የሰጠኻ
ቸው ።
ለበጎ ፡ ተስፋ ፡ መሐላን ፡ ቃል ፡ ኪዳንን ፡ ለሰጠ ፳፩፤
ሀቸው ፡ ለልጆችህ ፡ ምን ፡ ያህል ፡ ተጠንቅቀህ ፡
ትፈርድላቸው ፡ ይሆን ፡ እኛን ፡ እየመከርህ ።
በፈረድህባቸው ፡ ጊዜ ፡ ቸርነትህን ፡ እናስብ ፡ ፳፪፤
ዘንድ ፡ አንተንም ፡ እንመስል ፡ ዘንድ ፡ ጠላቶቻ
ችንን ፡ በብዙ ፡ መቻያ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ወዲህም ፡
እኛን ፡ እየመከርህ ፡ ጠላቶቻችንን ፡ ታጠፋለህ ።
በፈረድህብንም ፡ ጊዜ ፡ ይቅርታህን ፡ ተስፋ ፡ ፳፫፤
እናደርጋለን ፡ በኃጢአት ፡ በስንፍና ፡ ዘመንን ፡
የኖሩ ፡ በደለኞች ፡ ሰዎችን ፡ በዚህ ፡ ቀጣህ ።
በጠገባቸው ፡ ያሉ ፡ የተዋረዱ ፡ ከብቶችን ፡ አማ ፳፬፤
ልክት ፡ እያሉ ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ በስሕተት ፡ ሥራ ፡
ተጐድተዋልና ፡ በየራሳቸው ፡ ኃጢአት ፡ ፈረ
ድህባቸው ።
እውቀት ፡ እንደሌላቸው ፡ እንደ ፡ ልጆች ፡ አሰት ፡ ፳፭፤
ተናገሩ ። ስለዚህ ፡ ነገር ፡ አእምሮ ፡ እንደሌላ
ቸው ፡ እንደ ፡ ሕፃናት ፡ ስለሆኑ ፡ እንደ ፡ ጥዛቸው ፡
መጠን ፡ መቻያን ፡ በነሳቸው ፡ አመጣህ ።
ፈርዶ ፡ በመጣው ፡ በሥሩ ፡ መቅሠፍት ፡ ከልተ ፳፮፤
መለሱ ፡ በገኛቸው ፡ መከራ ፡ እነዚህ ፡ እንጉራ
ጉረዋልና ፡ ቸልም ፡ ብለዋልና ፡ የባሕርይ ፡ አም
ላክ ፡ የሚሆን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ አምበሻ ፡
ስጥመትን ፡ ይቀምሱ ።
አማልክት ፡ ብሏቸው ፡ በኒህ ፡ በጣዖታቱ ፡ በተ ፳፯፤
ፈረደባቸው ፡ ጊዜ ፡ ቀድሞ ፡ የካዱት ፡ ፈጣሪያ
ቸውን ፡ ያውቁታል ፡ እርሱ ፡ ፈጣሪያቸው ፡
እንደ ፡ ሆነ ፡ በውነት ፡ ያውቁታል ። ስለዚህም ፡
ነገር ፡ ያሥሩ ፡ መቅሠፍት ፡ ፍጻሜ ፡ የሚሆን ፡
ስጥመት ፡ ደረሰባቸው ።

ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

እግዚአብሔርን ፡ የማወቅ ፡ አጐዳደል ፡ በል ፩፤
ቡናቸው ፡ ያለባቸው ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ በውነት ፡
ከንቱ ፡ ናቸውና ፡ በኒህ ፡ በሚታዩ ፡ ፍጥረቶች ፡
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ያለ ፡ እርሱን ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ፡
ተሳናቸው ፡ ሥራውንም ፡ እያዩ ፡ እኒህ ፡ ፈጣሪ
ያቸውን ፡ አላወቁም ።

፪ ፈጥኖ ፡ የሚነፍስ ፡ ነፋስንና ፡ እሳትን ፡ የሚዞሩ ፡
ከዋክብትንም ፡ ገንተቶ ፡ የሚሄድ ፡ ውኃን ፡
ለዓለሙ ፡ ሊያበሩ ፡ የተፈጠሩ ፡ ከዋክብትንና ፡
ፀሐይን ፡ አማልክትን ፡ አስመሰሏቸው ፡ እንጂ ፡
ፈጣሪያቸውን ፡ አላወቁም ።
፫ በብርሃናቸው ፡ ማማር ፡ ደስ ፡ በላቸው ፡ ጊዜ ፡
እንደዚህን ፡ ጨረቃና ፡ ፀሐይን ፡ አማልክት ፡
ካደረጉዋቸው ፡ ብርሃን ፡ የፈጠረ ፡ እርሱ ፡ ይህ
ንን ፡ ፍጥረት ፡ ፈጥሯልና ፡ የነዚህ ፡ ፈጣሪ ፡
ፈጽሞ ፡ እንዲበልጥ ፡ ይወቁ ።
፬ ከብርሃናቸውና ፡ ከሙቀታቸው ፡ የተነሣ ፡ ከተደ
ነቁስ ፡ የፈጠራቸው ፡ እርሱ ፡ ፈጽሞ ፡ እንዲበ
ልጥ ፡ ልብ ፡ ያድርጉ ።
፭ አከናውኖ ፡ የፈጠራቸው ፡ ሰዎች ፡ ፀሐይ ፡ ጨረ
ቃን ፡ አይተው ፡ የፈጠራቸው ፡ እግዚአብሔ
ርን ፡ በፀሐይ ፡ በጨረቃ ፡ የመሰሉት ፡ በውኑ ፡
የፀሐይ ፡ የጨረቃ ፡ ብርሃን ፡ በሱ ፡ ዘንድ ፡ አለ ።
፮ ነገር ፡ ግን ፡ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ ዳግመኛ ፡ በሳቸው ፡
ያለ ፡ ነቀፋ ፡ ጥቂት ፡ አይደለም ፡ በሳቱ ፡ ጊዜ ፡
ፈጣሪን ፡ እየፈለጉት ፡ ያገኙትም ፡ ዘንድ ፡ እየ
ወደዱ ፡ ፀሐይ ፡ ጨረቃን ፡ ወደ ፡ መመርመር ፡
ተመልሰው ፡ እነሳቸው ፡ በፈለጉት ፡ ነበር ፡
ተብሎ ፡ ይፈረድባቸዋልና ፡ እንጂ ፡
፯ በነሱ ፡ ያለ ፡ ነቀፋ ፡ ጥቂት ፡ አይደለም ፡ የሚ
ታዩ ፡ ጨረቃና ፡ ፀሐይ ፡ ያማሩ ፡ የተወደዱ ፡
ናቸውና ፡ ፀሐይ ፡ ጨረቃን ፡ በማየት ፡ አበቁ ።
፰ ዳግመኛም ፡ ምክንያታቸው ፡ ብዙ ፡ ነው ።
፱ ዓለምን ፡ ማወቅ ፡ መረዳት ፡ እስኪገባቸው ፡
ድረስ ፡ ያዩ ፡ ዘንድ ፡ በዚህስ ፡ ሥራ ፡ ይህን ፡
ያህል ፡ ከተቻላቸው ።
፲ የፀሐይና ፡ የጨረቃን ፡ ፈጣሪ ፡ መርምረው ፡ ያገ
ኙት ፡ ዘንድ ፡ እንዴት ፡ አልተቻላቸው ፡ ተብሎ ፡
ይፈረድባቸዋልና ፡ እነሳቸውስ ፡ ጐስቋሎች ፡
ናቸው ፡ የሰው ፡ እጅ ፡ ሥራን ፡ በሥራ ፡ መራ
ቀቅ ፡ ከብርና ፡ ከወርቅ ፡ የሠሯቸውን ፡ አማል
ክት ፡ ብለው ፡ ያመሰገኑ ፡ የነዚህ ፡ በሥራም ፡
አለኝታቸው ፡ አላፊ ፡ ነው ። የእንስሳን ፡ ምስል ፡
የሚረባ ፡ የሚጠቅም ፡ የቀደመ ፡ የእጅ ፡ ሥራ ፡
የሚሆን ፡ ደንጊያውንም ፡ አማልክት ፡ ያለው ፡
ያመሰገኑ ፡ የነዚህ ፡ አለኝታቸው ፡ አላፊ ፡ ነው ።
፲፩ የቆመውን ፡ የተጋደመውን ፡ እንጨት ፡ የሚ
ጠርብ ፡ ጠራቢ ፡ ቢኖር ፡ በን ፡ ሆኖ ፡ የበቀለውን ፡
እንጨት ፡ ቈርጦ ፡ ቅርፊቱን ፡ ሁሉ ፡ ጠርበ
ታልና ።
፲፪ በጎ ፡ አድርጎ ፡ ተራቀበታልና ፡ ለኑሮ ፡ አገልጋይ ፡
ሊሆን ፡ የሚረባ ፡ ዕቃን ፡ አድርጎ ፡ ሠርቶታልና ፡
ለምግብ ፡ አገልጋይ ፡ ሊሆን ፡ በማውጣጣት ፡
ሥራውን ፡ ጠርቦ ፡ ጨርሷልና ፡ ይህን ፡ ሽጦ ፡
ለውጦ ፡ ጠገበ ።
፲፫ ዳግመኛ ፡ ለምንም ፡ ለምን ፡ ከማይረባ ፡ እን
ጨት ፡ የተረፈ ፡ ጉማጁን ፡ ይኸውም ፡ ቍጥር
ጥር ፡ ያለ ፡ ነው ፡ ከሥሩ ፡ እስከ ፡ ጫፉ ፡ ድረስ ፡
ሁለንተናው ፡ ጠማማ ፡ ነው ፡ ሥራውን ፡ በማስ
ትንተን ፡ ወስዶ ፡ ጠርቦ ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በበዛን
በት ፡ ቀን ፡ ቀረጸው ፡ በሰው ፡ አምሳልም ፡ መሰ
ለው ።
ከንቱ ፡ በሚሆን ፡ በእንስሳ ፡ ምስልም ፡ አስመ ፲፬
ሰለው ፡ ጥቁር ፡ ቀለም ፡ ቀባው ። በጣቱም ፡ ቀይ ፡
ቀለም ፡ አግብቶ ፡ ቀይ ፡ አደረገው ። የሱ ፡ እድፍ ፡
የሚሆን ፡ ቀለምንም ፡ አገባው ።
ለሱ ፡ የሚገባው ፡ ተመትቶ ፡ የተሠራ ፡ ቤት ፡ ፲፭
ሠራ ፡ በሠራለት ፡ በታ ፡ አኖረው ፡ ከኖራው ፡
አስጠግቶ ፡ በብረት ፡ ቸነከረው ።
ምስል ፡ ነውና ፡ የሚረዳው ፡ ይፈልጋልና ፡ ፲፮
ራሱን ፡ መርዳት ፡ እንዳይችል ፡ አውቆ ፡ እንዳ
ይወድቅበት ፡ አስተነተነ ።
እንደዚህ ፡ አድርጎ ፡ ሠርቶ ፡ በሱ ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ፲፯
ገንዘቡ ፡ ስለ ፡ ሚስቱ ፡ ስለ ፡ ልጆቹ ፡ ይለምናል ፡
ነፍስ ፡ ከሌለው ፡ ከጣዖቱ ፡ ጋራ ፡ ሲነጋገር ፡ አያ
ፍርም ።
ከበሽተኛ ፡ ከጣዖቱ ፡ ዘንድ ፡ የድኅነትን ፡ ነገር ፡ ፲፰
ይለምናል ። ስለ ፡ ሕይወትም ፡ ምውት ፡ ጣዖ
ትን ፡ ይለምናል ፡ አእምሮ ፡ ከሌለው ፡ ከጣዖቱ ፡
ዘንድ ፡ የንብረትን ፡ ነገር ፡ ይማልዳል ፡ ይለም
ናል ።
የመንገድንም ፡ አካሄድ ፡ ነገር ፡ ይንቀሳቀስ ፡ ፲፱
ዘንድ ፡ የማይቻለው ፡ አንዲት ፡ እርምጃን ፡ ከማ
ይራመድ ፡ ከጣዖቱ ፡ ዘንድ ፡ ይለምናል ። የሥ
ራንና ፡ የብዕልን ፡ ነገር ፡ ገንዘብ ፡ የማግኘትን ፡
ነገር ፡ ይለምናል ። የእጅን ፡ ሥራ ፡ ለማቅናት ፡
እጆቹ ፡ ምንምን ፡ ከማይሠሩ ፡ ከጣዖቱ ፡ ዘንድ ፡
ይለምናል ። ሥራንም ፡ ማፋጠን ፡ ከርሱ ፡ ይፈ
ልጋል ።

ምዕራፍ ፡ ፲፬ ።

ክፉ ፡ በሆኑ ፡ በማዕበላቱ ፡ መካከል ፡ ሊሔድ ፡ ፩
ወዶ ፡ በመርከብ ፡ ሰውን ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ በላከ ፡
ጊዜ ፡ ዳግመኛ ፡ ይለምናል ፡ ከምትሸከመው ፡
ከመርከቢቱ ፡ የሚደክም ፡ ከሚዋረድ ፡ ከጣ
ዖቱ ፡ ዘንድ ፡ ይለምናል ።
ትርፍ ፡ በመውደድ ፡ ይህንን ፡ ጣዖቱን ፡ ሠርቶታ ፪
ልና ፡ ብልህም ፡ በጥበቡ ፡ ሠርቶታልና ፡ ከምት
ሸከመው ፡ ከመርከቢቱ ፡ ከሚደክም ፡ ከሚዋ
ረድ ፡ ከጣዖት ፡ ዘንድ ፡ ይለምናል ።
መምህር ፡ አብ ፡ ሆይ ፡ ያንተ ፡ ሥልጣን ፡ ግን ፡ ፫
ሁሉን ፡ ትሠራራለች ፡ በባሕር ፡ መንገድን ፡ ሰጥተ
ሃልና ፡ በውኑት ፡ ሁሉን ፡ ማዳን ፡ እንዲቻልህ ፡
መጠን ፡ በሞገዱ ፡ መካከል ።
ጽኑ ፡ ፍለጋን ፡ ታሳያለህና ፡ ወደ ፡ መርከብም ፡ ፬
በማውጣት ፡ ኖኅን ፡ አድነሃልና ።
የጥበብህ ፡ ምሥጢርዋ ፡ የበዛ ፡ እንዳይሆን ፡ ፭
ስለወደድክ ፡ ዳግመኛ ፡ ያለመርከብ ፡ አሳልፈሃ
ልና ፡ (እስራኤል ፡) ያንተ ፡ ሥልጣን ፡ ግን ፡
ሁሉን ፡ ትሠራራለች ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ሰዎች ፡
ሰውነታቸውን ፡ በተናቀ ፡ በተዋረደ ፡ እንጨት ፡
ይታመናሉ ፡ በታላቅና ፡ በታናሽ ፡ መርከብ ፡
በሞገዱም ፡ መካከል ፡ ተሻግረው ፡ ይድናሉ ።
ቀድሞም ፡ ትዕቢተኞች ፡ የሚሆኑ ፡ ረዓይት ፡ ፮

በጠፋ ፡ ጊዜ ፡ የዓለም ፡ ተስፋ ፡ የሚሆን ፡ ኖኅ ፡
በመርከብ ፡ሸሽም ፡ሆኖ ፡ተጠግቶ ፡ ዳነ ፡ በንተ ፡
ሥልጣን ፡ ተቀሥሮ ፡ የሰውንም ፡ ዘርዕ ፡ ለዓለም ፡
ተወ ።
፯፡ ጽድቅ ፡ በሚሠራበት ፡ ገንዘብ ፡ ይህ ፡ መርከብ ፡
ተባርኳልና ፡ በመርከብ ፡ ዳነ ።
፰፡ በስንፍና ፡ የተሠራ ፡ ይህ ፡ ጣዖቱ ፡ ግን ፡ የተረ
ገመ ፡ነው ፡ የሠራውም ፡ የተረገመ ፡ ነው ፡ ይህ ፡
ሥራ ፡ የሚጠፋ ፡ ሥራ ፡ ነውና ፡ የሚጠፋ ፡
አምላክ ፡ ተባለ ።
፱፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ሥራውና ፡ ሠሪው ፡
በትክክል ፡ ስለተጠሉ ።
፲፡ የተሠራው ፡ ሥራ ፡ ከሠሪው ፡ ጋራ ፡ ይፈረድ
በታልና ።
፲፩፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ በአሕዛብ ፡ ጣዖት ፡ ምርመራ ፡
ይደረጋል ።
፲፪፡ ይህ ፡ ጣዖቱ ፡ ሰውን ፡ ለማጥፋት ፡ ተሠርቷልና ፡
ለሰዎችም ፡ ሰውነቶች ፡ መሰናከል ፡ ሆኖ ፡ ተሠ
ርቷልና ፡ ለሰነፎች ፡ ሰዎች ፡ እግረ ፡ ልቡናቸ
ውን ፡ ሊያሰናክል ፡ ተሠርቷልና ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡
ምርመራ ፡ ይሆናል ፡ የዝሙት ፡ መጀመሪያው ፡
ጣዖት ፡ ልሥራ ፡ ብሎ ፡ ማሰብ ፡ ነውና ።
፲፫፡ ይህን ፡ ጣዖቱን ፡ ማግኘት ፡ የሰውነት ፡ ጥፋቷ
ነው ። ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ አልነበረምና ፡ ለዘለዓ
ለሙም ፡ አይኖርምና ።
፲፬፡ በሞት ፡ ተነጥቀው ፡ የመሄዳቸውን ፡ ፍጻሜ ፡
የሚያፋጥን ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ከንቱ ፡ ሰው ፡ በሚሆን ፡
በክብሩ ፡ ምክንያት ፡ ከንቱ ፡ ጣዖት ፡ ወደዚህ ፡
ዓለም ፡ ገባ ።
፲፭፡ ልጁ ፡ሕፃን ፡ሳለ ፡ ፈጥኖ ፡ በሞት ፡ ስለ ፡ ተነጠቀ ፡
ሲሩህ ፡ ላንድ ፡ ልጁ ፡ ይፃፃር ፡ ያለቅስ ፡ ነበርና ፡
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ጣዖት ፡ መሥራትን ፡ አሰቡ ።
ለሞተ ፡ ሰው ፡ ክብሩ ፡ ቀድሞ ፡ የሠሩለት ፡ ምስ
ሉን ፡ ዛሬ ፡ እንደ ፡ አምላክ ፡ አድርገው ፡ አከበ
ሩት ። ለኃጢአት ፡ የተገዙ ፡ ሰዎች ፡ በገሃድ ፡
በዓል ፡ አደረጉለት ፡ በምሥጢርም ፡ መሥዋ
ዕት ፡ ሠሩለት ።
፲፮፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በዘመን ፡ መራቅ ፡ የገዝንጋኤና ፡
የበደል ፡ ልማድ ፡ ሥርዓት ፡ ሆኖ ፡ ተያዘ ፡ እንደ ፡
ሕግም ፡ አድርገው ፡ ጠበቁት ። ክፉዎች ፡ በሆኑ ፡
በመኳንንት ፡ ትእዛዝም ፡ ጣዖታትን ፡ አመለኳ
ቸው ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ቢያከብሯቸው ፡ የማይቻ
ላቸው ፡ ሰዎችንም ፡ አመለኳቸው ።
፲፯፡ በሩቅ ፡ አሉና ፡ መልካቸውንም ፡ ቀረጡ ። መልኩ ፡
በሩቅ ፡ ሳለ ፡ በነርሱ ፡ ዘንድ ፡ ክቡር ፡ ለሚሆን ፡
ለንጉሥ ፡ የሌለውን ፡ እንዳለ ፡ አድርገው ፡ የኃላ ፡
ሥልጣን ፡ ሠሩለት ።
፲፰፡ ተግተውም ፡ ይለምናሉ ። ስሕተታቸውንም ፡
ያላወቁ ፡ ሰዎች ፡ በአምልኮታቸው ፡ ጸኑ ። የእ
ግዚአብሔርንም ፡ ክብር ፡ የሰው ፡ እጅ ፡ ሥራ ፡
ወደሚሆን ፡ ወደ ፡ ጣዖቱ ፡ መለሱ ።
፲፱፡ ዳግመኛ ፡ የሚገዛ ፡ ንጉሡን ፡ አድልቶ ፡ ደስ
ያሰኘው ፡ ዘንድ ፡ የሚወድ ፡ አለ ። በሚያምር ፡
በሚበልጥ ፡ ገንዘብ ፡ ምስሉን ፡ በመሥራት ፡
ተራቀቀ ።
በሥራውም ፡ መልክ ፡ ማማር ፡ ደስ ፡ ስላላቸው ። ፳፡
ብዙ ፡ ሰዎች ፡ በዚህ ፡ ተሳቡ ፡ ከጥቂትም ፡
ቀን ፡ አስቀድሞ ፡ በትንሽ ፡ ክብር ፡ የነበረ ፡
ሰውን ፡ ዛሬ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ አምላክ ፡ አደረጉት ።
በችግር ፡ በግድ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ተገዝቷልና ፡ ፳፩፡
ይህ ፡ ጣዖቱ ፡ ለሰው ፡ መሰናክል ፡ ሆነ ፡ ለሥራ ፡
ቢሆኑ ፡ ከሚጠቅሟቸው ፡ ከደንጊያና ፡ ከእን
ጨት ፡ ጋራ ፡ አንድነት ፡ የሌለው ፡ የፈጣሪን ፡
ስም ፡ ለደንጊያና ፡ እንጨቶች ፡ አደረጉ ።
እግዚአብሔርን ፡ ከለማወቃቸው ፡ ጋራ ፡ ስሕተ ፳፪፡
ታቸው ፡ አልበቃቸውምና ፡ ልጆቻቸውን ፡ ለጣ
ዖት ፡ ይሠዋሉና ።
ይህን ፡ ያህል ፡ ዘመን ፡ በስንፍና ፡ የኖሩ ፡ በጽኑ ፡ ፳፫፡
ሰልፍ ፡ ሳሉ ፡ እንዲህ ፡ ክፉ ፡ የሚሆን ፡ ጣዖትን ፡
ገናና ፡ አምላክ ፡ ያደረጉት ፡ የፍቅር ፡ አምላክም ፡
ያሉት ፡ እነዚህ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ከለማወቃ
ቸው ፡ ጋራ ፡ ስሕተታቸው ፡ አልበቃቸውም ።
ዳግመኛ ፡ የተሠወረ ፡ ምሥጢርንም ፡ ይሠራሉ ፡
እንጂ ፡ ይህም ፡ ባይሆን ፡ ከሕጋቸው ፡ ወጥተው ፡
በሌላ ፡ ሥርዓት ፡ እየተቅበዘበዙ ፡ ያስቡ ፡ ዘንድ ።
በልንጀራ ፡ ባልንጀራውን ፡ ይገድለዋል ፡ እንጂ ፡ ፳፬፡
ይህም ፡ ባይሆን ፡ ያቡበለዋል ፡ በሽተኛም ፡ በሚ
ያደርገው ፡ ገንዘብ ፡ ተስፋ ፡ ይሰጠዋል ፡ እንጂ ፡
ፈጽመው ፡ ሕጋቸውን ፡ የግቢ ፡ ሥራቸውን ፡
አልጠበቁም ።
ሥራዎቻቸው ፡ ሁሉ ፡ ደም ፡ ከማፍሰስ ፡ ጋራ ፡ ፳፭፡
ነፍስ ፡ ከመግደል ፡ ጋራ ፡ ከመስረቅ ፡ ጋራ ፡ ከሐ
ሰት ፡ ጋራ ፡ ከጥፋት ፡ ጋራ ፡ ምስጋናን ፡ ከማጉ
ደል ፡ ጋራ ፡ ከሰማመን ፡ ጋራ ፡ በሐሰት ፡ ከመ
ማል ፡ ጋራ ።
በጎውን ፡ ሰው ፡ ከማወክ ፡ ጋራ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፳፮፡
የሚሰጠውን ፡ ዋጋ ፡ ከለማሰብ ፡ ጋራ ፡ ሰውነቱን ፡
ከማስተዳደፍ ፡ ጋራ ። ፍጥረትን ፡ ከመለወጥ ፡
ጋራ ፡ የግቢን ፡ ሥርዓት ፡ ከማፍረስ ፡ ጋራ ፡ ከም
ንዝር ፡ ጋራ ፡ ከሚያጸይፍ ፡ ሥራ ፡ ጋራ ፡ የተቀ
ላቀለ ፡ ነው ።
ስም ፡ የሌላቸው ፡ ጣዖቶችን ፡ ማምለክ ፡ የክ ፳፯፡
ፋት ፡ ሁሉ ፡ መጀመሪያ ፡ ነውና ፡ የኃጢአትም ፡
ፍጻሜ ፡ ነውና ፡ የሚያመልኳቸው ፡ ሰዎች ፡ እን
ደነዚህ ፡ ደስ ፡ ቢላቸው ፡ አእምሮአቸውን ፡ ያጣ
ሉና ፡ ልጆቻቸውን ፡ ይሠዋሉ ።
ይህም ፡ ባይሆን ፡ ሐሰት ፡ ነገርን ፡ ይናገራሉ ፡ ፳፰፡
ይህም ፡ ባይሆን ፡ ይሞት ፡ በቃውን ፡ ያድናሉ ፡
ይህም ፡ ባይሆን ፡ በሐሰት ፡ ፈጥነው ፡ ይምላሉ ።
ሁሉን ፡ እንደሚያውቅ ፡ እንደ ፡ ፈጣሪ ፡ ቃል ፡ ፳፱፡
እውቀት ፡ ያላቸው ፡ እነዚህ ፡ ነፍስ ፡ የሌለው ፡
ሐሰተኛ ፡ ድዳ ፡ ጣዖትን ፡ ይታመናሉና ፡ በዚህ ፡
በጣዖቱ ፡ ቢምሉ ፡ ይፈርድባቸው ፡ ዘንድ ፡
ተስፋ ፡ አያስቡምና ።
በውነት ፡ የሚሆን ፡ መቻያ ፡ አንድነት ፡ ያገኛቸ ፴፡
ዋል ፡ ጣዖቱን ፡ በተመለከቱ ፡ ጊዜ ፡ በእግዚአ
ብሔር ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡ አሰበዋልና ፡ የፈጣሪን ፡
እውነተኛ ፡ ሕጉን ፡ ንቀው ፡ አቃለው ፡ በግፍ ፡

በሐሰት ፡ ምለውበታልና ።
፴፩ እውነት ፡ የሚሆን ፡ መቻያ ፡ ያገኛቸዋል ። በኃ
ጢአታቸው ፡ የተፈረደባቸውን ፡ ፍርድ ፡ ለማ
ሳለፍ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ኃይሉን ፡ ይገልጥብናል ፡
ሲሉ ፡ የማሉ ፡ አይደለምና ። ሁለጊዜ ፡ ሰውን ፡
በሚበድሉ ፡ በወንጀላቸው ፡ ላይ ፡ መቻያ ፡ ትም
ጣባቸው ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፭ ።

፩ አንተ ፡ ፈጣሪያችን ፡ ግን ፡ ቸር ፡ ነህ ፡ ይቅር ፡
ባይ ፡ ነህ ፡ የምትታገሥ ፡ ነህ ። ከሀሊነትህን ፡
እያወቅን ፡ ብንበድል ፡ ባንበድልም ፡
፪ ያንተ ፡ ወገኖች ፡ ነንና ፡ በቸርነትህ ፡ ሁሉን ፡ ትሠ
ራለህ ። ነገር ፡ ግን ፡ ያንተ ፡ ወገኖች ፡ እንደ ፡
ሆንን ፡ እናውቃለንና ።
፫ አንተንም ፡ ማወቅ ፡ ፍጹም ፡ ክብር ፡ ናትና ፡ አን
ተንም ፡ ማወቅ ፡ የነፍስ ፡ ሕይወት ፡ ናትና ።
፬ የሰው ፡ ጥበብ ፡ የሚሆን ፡ በጣዖት ፡ ክፉ ፡ ልቡና ፡
አያስተንምና ፡ ይኸውም ፡ የሌለው ፡ ጌጥ ፡
ያለው ፡ ድካም ፡ ነው ፡ ቀለም ፡ በመቀባት ፡
መልካቸው ፡ የሚለዋወጥ ፡ የሰው ፡ ሥራ ፡ የሚ
ሆን ።
፭ ወዶ ፡ ይመጣ ፡ ዘንድ ፡ አላዋቂን ፡ ሰው ፡ መል
ካቸው ፡ የሚስበው ፡ አያስተንምና ፡ ነገር ፡ ግን ፡
ነፍስ ፡ መንቀሳቀስ ፡ የሌለው ፡ ምውት ፡ ጣዖ
ትን ፡ ይወዳል ።
፮ እኒህ ፡ ክፋትን ፡ የሚወዱ ፡ ናቸው ፡ ወደው ፡
ለሚሠሩዋቸው ፡ ለሚያመልኳቸውም ፡ እንደ
ዚህ ፡ ያለ ፡ ተስፋ ፡ ይገባቸዋል ።
፯ ሠራተኛ ፡ የለሰለሰ ፡ ጭቃን ፡ በለወሰ ፡ ጊዜ ፡
ከኛ ፡ ላንዱም ፡ ላንዱም ፡ ሁሉ ፡ ሊያገለግል ፡
የሚገባውን ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ሥራ ፡ ይሠራል ፡
ነገር ፡ ግን ፡ ከዚያ ፡ ከጭቃ ፡ ንጹሕ ፡ ለሆኑ ፡ ሥራ
ዎች ፡ አገልጋይ ፡ ሊሆን ፡ ንጹሕ ፡ ሥራዎችን ፡
ይሠራል ፡ ለሌላዎችም ፡ ሥራዎች ፡ በነዚህ ፡
አምሳል ፡ እንደነዚህ ፡ አድርጎ ፡ ይሠራል ፡ የነ
ዚህ ፡ ሁሉ ፡ ሥራቸው ፡ ያንዱም ፡ ያንዱን ፡
ፈቃድ ፡ ለመፈጸም ፡ ነው ። ይህንንም ፡ ጭቃ ፡
የሚሠራ ፡ ሰው ፡ እውነት ፡ ፍርድን ፡ የሚፈ
ርድ ፡ ዳኛ ፡ ነው ።
፰ ለክፋት ፡ የሚደክም ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ከዚያ ፡ ከጭቃ ፡
ከንቱ ፡ ጣዖትን ፡ ይሠራል ። ይህም ፡ ከጥቂት ፡
ቀን ፡ አስቀድሞ ፡ ከምድር ፡ ተሠራ ፡ ከጥቂት ፡
ቀንም ፡ በኋላ ፡ ከርሷ ፡ ወደ ፡ ተገኘው ፡ ወደ ፡
ምድር ፡ ይመለስ ፡ ዘንድ ፡ አለው ። ስለሰውነቱ ፡
ፍርድ ፡ ይመረምሩታል ። (ሥላሴ ፡)
፱ ፈጽሞ ፡ ይደክም ፡ ዘንድ ፡ አለውና ፡ ነገር ፡ ግን ፡
ከርሱ ፡ ዘንድ ፡ ያለው ፡ ትጋቱ ፡ ሳያውቅ ፡ አይ
ደለም ። ወርቅና ፡ ብርን ፡ የሚሠሩ ፡ ሰዎችን ፡
ይቀዋወማቸው ፡ ናስንም ፡ የሚሠሩ ፡ ሰዎችን ፡
ይመስላቸው ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ አነዋወሩ ፡
ጥቂት ፡ ቀን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ሳያውቅ ፡ አይደለም ።
ይህን ፡ የጕሰቈለ ፡ ጣዖትን ፡ ከሠራ ፡ በኋላ ፡
ክብርን ፡ ይሰጠዋል ።
የእንደዚህ ፡ ያለው ፡ ሰው ፡ ልቡናው ፡ አመድ ፡ ፲
ነው ፡ አለኝታውም ፡ ከመሬት ፡ ይልቅ ፡ አለኝ
ታው ፡ ይጐሰቊላል ፡ የፈጠረውን ፡ የምታሠለ
ጥን ፡ አዋቂ ፡ የደመ ፡ ነፍስንም ፡ ሕይወት ።
የምትሆን ፡ ነፍስን ፡ ያዋሀደው ፡ ፈጣሪውን ፡ ፲፩
አላወቀምና ፡ ፈጽሞ ፡ አነዋወሩ ፡ ከጭቃ ፡
ይልቅ ፡ ይናቃል ።
ነገር ፡ ግን ፡ እነዚህ ፡ ዘመናችንን ፡ ዋዛ ፡ ፈዛዛ ፡ ፲፪
አድርገው ፡ አሰቡ ፡ አነዋወራችንንም ፡ ለትርፍ ፡
ምልክት ፡ አደረጉት ፡ ጣዖት ፡ ስላጣሁ ፡ ይጨን
ቀኛል ፡ ብኋልና ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ይከብራል ፡
ጣዖት ፡ ይገዛል ።
በምድር ፡ ከሚታየው ፡ ፈጥኖ ፡ ከሚጠፋው ፡ ፲፫
ከእንጨት ፡ የተቀረጠ ፡ ጣዖትን ፡ ሠርቷልና ።
ከሁሉ ፡ ፈጽሞ ፡ ይህ ፡ እንዲከፋ ፡ ፈጽሞ ፡
ታወቀ ።
ነገር ፡ ግን ፡ ሁሉም ፡ አላዋቆች ፡ ጕስቋሎች ፡ ፲፬
ናቸው ፡ ከተማረኩ ፡ ወገኖች ፡ የሚሆኑ ፡ እነ
ዚህ ፡ ሁሉ ፡ ከእውቀት ፡ የተለዩ ፡ ናቸው ፡ በጣ
ዖቱ ፡ የጸኑ ፡ ሰዎች ፡ ከሕፃናቱ ፡ ሰውነት ፡ ይልቅ ፡
ስንፍናን ፡ ያበዛሉ ።
መሥራት ፡ የማይቻላቸው ፡ የአሕዛብን ፡ ጣዖ ፲፭
ቶች ፡ አማልክት ፡ አድርገው ፡ አሰበዋልና ፡ በዓ
ይናቸው ፡ ማየት ፡ በፍንጫቸው ፡ ነፍስን ፡ ለማ
ሽተት ፡ በጆሮአቸው ፡ መስማት ፡ በጆቻቸው ፡
ጣት ፡ መዳሰስ ፡ የማይቻላቸው ፡ እግሮቻቸ
ውም ፡ ከመሔድ ፡ የበዘኑ ፡ የአሕዛብን ፡ ጣዖ
ቶች ፡ አማልክት ፡ አድርገው ፡ አሰበዋልና ፡
ከሕፃናቱ ፡ ሰውነት ፡ ይልቅ ፡ ስንፍናን ፡ ያበዛሉ ።
ሰው ፡ ሠርቷቸዋልና ፡ ከአዳም ፡ የተከፈለ ፡ ፲፮
ሰውም ፡ ሠርቷቸዋልና ፡ አስመስሎ ፡ አምላ
ክን ፡ ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ ለሰው ፡ አይቻለውምና ።
እሱ ፡ ፈራሽ ፡ በስባሽ ፡ ሲሆን ፡ ኃጢአት ፡ በሚ ፲፯
ስማማው ፡ እጅ ፡ ምውት ፡ ጣዖትን ፡ ይሠራል ፡
እሱ ፡ ደኅነኛ ፡ ነውና ፡ እነዚህ ፡ ግን ፡ ፈጽሞ ፡
ደኅነኞች ፡ አይደሉምና ፡ ከነዚህ ፡ ከጣዖቶቹ ፡
ስለ ፡ ተሻለ ፡ ጣዖት ፡ ይሠራል ።
እንስሳዎችንም ፡ በስንፍና ፡ አማልክት ፡ ያደረ ፲፰
ጓቸው ፡ እንዚህ ፡ በስንፍና ፡ ያመልኳቸዋል ።
እነዚህን ፡ ግን ፡ በልቡና ፡ ቢመረምሯቸው ፡
ከሌሎች ፡ አማልክት ፡ ይከፋሉ ።
ፈቃዱን ፡ መፈጸም ፡ የወደደ ፡ ሰው ፡ ከነዚህ ፡ ፲፱
በንዱ ፡ እንስሳ ፡ አካል ፡ እነሆ ፡ ፈቃዱን ፡ ፈጸመ ፡
በንዱ ፡ ወነጀለ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ክብሩ ፡ ምስ
ጋናው ፡ በዚህ ፡ ርቋልና ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፮ ።

ይገባቸዋልና ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ጣዖቶቻቸውን ፡ ፩
በሚመስሉ ፡ አጋንንት ፡ ጠፉ ፡ በብዙ ፡ በሚሆኑ ፡
ትንኞች ፡ ክፉ ፡ የሚሆኑ ፡ እነዚህ ፡ ተጨነቁ ።
በጠላቶቻቸው ፡ ፊት ፡ ለወዳጆችህ ፡ በጎ ፡ አደ ፪
ረግህላቸው ፡ ፈቃዳቸውን ፡ ሊፈጽሙበት ፡
ምግብ ፡ ሊሆናቸው ፡ ቻናሽ ፡ ሰጠኋቸው ።
ጣዕሙ ፡ ልዩ ፡ የሆነ ፡ መናንም ፡ ይበሉ ፡ ዘንድ ፡

ሰጠኋቸው ።
፫ ስለዚያ ፡ ግን ፡ መብልን ፡ ይበሉ ፡ ዘንድ ፡ በወ
ደዱ ፡ ጊዜ ፡ ነገር ፡ በነሳቸው ፡ ስለተላከባቸው ፡
ከመብላት ፡ ወደ ፡ አለመብላት ፡ ይመለሳሉ ።
የዘወትር ፡ ልማድ ፡ የሚሆን ፡ ምግብን ፡ ናቁ ።
እነሱ ፡ ግን ፡ ጭንቅ ፡ ባገኛቸው ፡ ጊዜ ፡ ጥቂ
ትም ፡ ወራት ፡ በዩ ፡ ጊዜ ፡ ጣዕሙ ፡ ልዩ ፡ ለሆነ ፡
ምግብ ፡ ተዘጋጁ ።
፬ ቸልተኞች ፡ ክፉዎች ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፡ ያስርኀራኊ ፡
በነሱ ፡ ላይ ፡ መቻያ ፡ ያደርስባቸው ፡ ዘንድ ፡
ጠላቶቻቸውም ፡ ብቻቸውን ፡ እንደ ፡ ተጨነቁ ፡
እኒህ ፡ ያው ፡ ዘንድ ፡ ሙሴ ፡ ጸልዮ ፡ አምጥቶብ
ቸዋልና ፡ የዘወትር ፡ የሚሆን ፡ ምግብ ፡ ናቁ ።
፭ ክፉዎች ፡ የሚሆኑ ፡ የአራዊት ፡ ቍጣ ፡ ቢመጣ
ባቸው ፡ ክፉዎች ፡ በሚሆኑ ፡ በምድር ፡ አው
ሬዎች ፡ እነከከስ ፡ ቢያልቁ ።
፮ ጥቂት ፡ ወራት ፡ ይቀጡ ፡ ዘንድ ፡ ታወኩ ፡ እንጂ ፡
ለዘለዓለሙ ፡ የጸናባቸው ፡ አይደለም ፡ የሕግህን ፡
ሥርዓት ፡ ያሳስባቸው ፡ ዘንድ ፡ ይህም ፡ ምል
ክት ፡ ድኅነት ፡ ሆናቸው ።
፯ ከነዚህ ፡ ድኖ ፡ የተመለሰ ፡ ሰው ፡ ሁሉን ፡ የም
ታድን ፡ ሆይ ፡ በንተ ፡ ስለ ፡ አመነ ።
፰ ዳነ ፡ እንጂ ፡ በማየት ፡ ብቻ ፡ የዳነ ፡ አይደለም ፡
በዚህ ፡ ፈተንካቸው ።
፱ የተቆናጣጭ ፡ ዝንብና ፡ ያንበጣ ፡ እነከከስ ፡ እነ
ዚህን ፡ አጥፍቷቸዋልና ፡ ከመከራው ፡ ሁሉ ፡
የምታድን ፡ አንተ ፡ እንደ ፡ ሆንክ ፡ አሳመንክ
ቸው ። በእንደዚህ ፡ ያለ ፡ ምሳሌ ፡ ልትፈርድብ
ቸው ፡ ይገባቸዋልና ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ለነፍሳቸውም ፡
ድኅነት ፡ አላገኙም ።
፲ በልጆችህ ፡ በእስራኤል ፡ ግን ፡ መርዝ ፡ ያለው ፡
የእባቦች ፡ ጥርስ ፡ በታዘዘ ፡ ጊዜ ፡ ቸርነትህ ፡
መጥቶላቸዋልና ፡ አዳናቸው ።
፲፩ ሕግህን ፡ ለማሰብ ፡ ይህንን ፡ መከራ ፡ ቀምሰዋ
ልና ። ፈጥነው ፡ በጽኑ ፡ ክህደት ፡ እንዳይወ
ድቁ ፡ ተአምራትህን ፡ ከማሰብ ፡ ወጥተው ፡ በመከ
ራና ፡ በሌላ ፡ ሥራ ፡ እንዳይወድቁ ፡ ፈጥነው ፡ ዳኑ ።
፲፪ አቤቱ ፡ ሁሉን ፡ የሚያድን ፡ ቃልህ ፡ አዳናቸው ፡
እንጂ ፡ የሚጠጡት ፡ እንጨት ፡ የሚቀቡት ፡
አስማት ፡ ያዳናቸው ፡ አይደለም ።
፲፫ ለሕይወትና ፡ ለሞት ፡ ሥልጣን ፡ አለህና ፡ ወደ ፡
መቃብር ፡ ታወርዳለህ ፡ ከመቃብርም ፡ ታወ
ጣለህ ።
፲፬ ሰው ፡ ግን ፡ በክፉ ፡ ይገድላል ፡ ነፍስ ፡ ከሥጋ ፡
ከተለየ ፡ በኋላ ፡ አይመለስም ፡ ከሥጋዋ ፡ የተለ
የች ፡ ነፍስ ፡ አትመለስም ።
፲፭ ከሥልጣንህ ፡ ግን ፡ ሸሽቶ ፡ መዳን ፡ አይቻልም ፡
ሸሽቼ ፡ አመልጣለሁም ፡ ማለት ፡ አይገባም ።
፲፮ ሕግህን ፡ የዘነጉ ፡ ሰዎች ፡ እንዲክዱህ ፡ ባወቅህ ፡
ጊዜ ፡ በሥልጣንህ ፡ ኃይል ፡ ተቀጥተው ፡ ጠፉ ።
በበረድና ፡ ልዩ ፡ በሆነ ፡ ዝናም ፡ ያለመገታትና ፡
ያስርኀራኊ ፡ በወረደ ፡ በሰማይ ፡ ሸሻቱ ፡ ጠፉ ፡
በእሳትም ፡ ጠፉ ።
ድንቅስ ፡ ሊመረምሩት ፡ የማይቻል ፡ ሥራ ፡ ፲፯
ይህ ፡ እሳት ፡ ለደጋጎች ፡ ረዳት ፡ ነውና ፡ በውኃ ፡
የሚጠፋ ፡ እሳት ፡ ሁሉ ፡ በውኃው ፡ መካከል ፡
ተደረገ ፡ ሠለጠነ ።
እግዚአብሔርን ፡ በዘነጉ ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ የተላከ ፡ ፲፰
የእሳት ፡ ማቃጠልን ፡ እንስሳትን ፡ እንዳያቃ
ጥል ፡ የለመደ ፡ ሆኗልና ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ይህንን ፡
በዩ ፡ ጊዜ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፍርድ ፡ እንዲጠፉ ፡
ያውቃሉ ።
በደለኛ ፡ የምትሆን ፡ የግብፅ ፡ ፍሬን ፡ ያጠፋ ፡ ፲፱
ዘንድ ፡ የእሳቱ ፡ ሠራዊት ፡ በውኃው ፡ መካከል ፡
ፈጽሞ ፡ ይነድ ፡ ነበር ።
ስለዚህ ፡ ስለ ፡ ፍሬው ፡ ፈንታ ፡ ያለቆችን ፡ ፳
ምግብ ፡ መገባቸው ፡ ያለድካም ፡ በሰማይ ፡ የተ
ዘጋጀ ፡ ከሚጣፍጠው ፡ ሁሉ ፡ ጣዕሙ ፡ የሚበ
ልጥ ፡ ጣዕሙን ፡ ሁሉ ፡ የሚያስንቅ ፡ ኅብስትን ፡
ሰደድክላቸው ።
የሰማያዊው ፡ መልክህ ፡ አርአያው ፡ መና ፡ ለል ፳፩
ጆችህ ፡ የፍቅርህን ፡ ምልክት ፡ ገለጠ ፡ ከዚህ ፡
ከመናው ፡ ለሚበላው ፡ ሰው ፡ ጣዕሙ ፡ ይዘዋ
ወር ፡ ነበር ፡ ከምግቡችም ፡ ወገን ፡ ያሰቡትም ፡ የወ
ደዱትን ፡ ለመፈጸም ፡ ፈጽሞ ፡ ያገለግላቸው ፡
ነበር ።
ውርጭና ፡ በረድ ፡ ከእሳት ፡ ጋራ ፡ ጸንተው ፡ ፳፪
ቆሙ ፡ እሳቲቱ ፡ በበረዱ ፡ መካከል ፡ እየነደደች ፡
በዝናሞችም ፡ መካከል ፡ በግ ፡ በግ ፡ እያለች ፡
ግብፃውያን ፡ የዘሩትን ፡ ፍሬያቸውን ፡ ፈጽማ ፡
እንዳጠፋች ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ፡ አልቀለጡም ።
እስራኤል ፡ ዳግመኛ ፡ ይህን ፡ በተመገቡ ፡ ጊዜ ፡ ፳፫
ራሳቸው ፡ የሚመገቡትን ፡ እርሻቸውን ፡ ተወ ።
ሁሉን ፡ የፈጠርህ ፡ ፍጥረቱ ፡ ሁሉ ፡ ላንተ ፡ ያገ ፳፬
ለግላልና ። የሚመልክ ፡ መቻያህን ፡ በግብፃው
ያን ፡ ላይ ፡ ታመጣለህ ፡ ወዲህም ፡ በንተ ፡ ወደ
ሚታመኑ ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ ይደርስ ፡ ዘንድ ፡
መናን ፡ ትሰጣለህ ።
ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ስጦታህ ፡ መና ፡ ወደ ፡ ሥራው ፡ ፳፭
ሁሉ ፡ እየተለዋወጠች ፡ በለመኑት ፡ በወደዱት ፡
ምግብ ፡ ሁሉ ፡ ታገለግል ፡ ነበር ።
አቤቱ ፡ በንተ ፡ ያመኑ ፡ ሰዎችን ፡ ቃልህ ፡ ይጠ ፳፮
ብቃቸዋል ፡ እንጂ ፡ ሰው ፡ የሚመገበው ፡ ልዩ ፡
ልዩ ፡ የሆነ ፡ የዘር ፡ ፍሬ ፡ ብቻ ፡ እንዳይደለ ፡
የወደድካቸው ፡ ልጆችህ ፡ እስራኤልን ፡ ያውቁ ፡
ዘንድ ፡ እየተለዋወጠች ፡ ታገለግላቸው ፡ ነበር ።
ብላሽ ፡ ሊሆን ፡ እሳት ፡ የሚያጠፋው ፡ መና ፡ ፳፯
በጥቂት ፡ ፀሐይ ፡ሙቀት ፡ ሞቆ ፡ ቀልጧልና ።
የሴሲንትህ ፡ ይታወቅ ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡ አንተን ፡ ፳፰
እናመሰግን ፡ ዘንድ ፡ ፀሐይ ፡ ከወጣ ፡ ዘንድ ፡
ወዳንተም ፡ እለምን ፡ ዘንድ ፡ ፀሐይ ፡ ወደኛ ፡
ይመጣ ፡ ዘንድ ፡ ይፈልጋልና ።
አንተን ፡ የማያመሰግን ፡ አለኝታው ፡ እንደ ፡ ፳፱
ክረምት ፡ ውርጭ ፡ የሚቀልጥ ፡ እንደማይረባ ፡
እንደሚያጸይፍ ፡ እንደ ፡ እጅ ፡ እጣቢ ፡ ውኃ ፡
የሚፈስ ፡ ስለ ፡ ሆነ ።

ምዕራፍ ፡ ፲፯ ።

፩ ፍርድህ ፡ ጽኑ ፡ ነውና ፡ ለመናገርም ፡ የሚያ
ስጨንቅ ፡ ነውና ። ስለዚህ ፡ ነገር ፡ የፈጣሪ ፡ ትም
ህርት ፡ የሌላቸው ፡ ሰውነቶች ፡ ሳቱ ።
፪ ግብፃውያን ፡ ደግ ፡ ወገን ፡ እስራኤልን ፡ በያዙ ፡
ጊዜ ፡ በተበረታቱባቸውም ፡ ጊዜ ፡ ረዥም ፡
በሚሆን ፡ በሌሊት ፡ ጨለማ ፡ እነዚህ ፡ ግብፃው
ያን ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ ከቤታቸው ፡ መከታ ፡ ስር
ታሥረው ፡ ተግዘዋልና ። የበደሉትን ፡ በደላቸ
ውን ፡ አስበው ፡ የዘለዓለም ፡ ከሚሆን ፡ አገልግ
ሎት ፡ ሥርዓት ።
፫ የሸሹ ፡ ሆነው ፡ ተገኙ ፡ በውስጡ ፡ ብርሃን ፡
በሌለበት ፡ ቤት ፡ በጨለማ ፡ ተሠውሮ ፡ አን
ዱም ፡ አንዱም ፡ ይዘነጋ ፡ ነበር ፡ ተበተኑ ፡
እጅግ ፡ እየተደነቁ ፡ በድንጋጤ ፡ የተነሣ ፡ እንደ ፡
ሰም ፡ ቀለጡ ።
፬ አመንዝራ ፡ የሚሆን ፡ ዲያብሎስ ፡ ያለድንጋጤ ፡
ይጠብቃቸው ፡ ዘንድ ፡ አልቻለም ፡ ነገር ፡ ግን ፡
ሰውነት ፡ ስግጥጥ ፡ ስግጥጥ ፡ የሚያደርግ ፡ ታላቅ ፡
የሚሆን ፡ የቃል ፡ ድምፅ ፡ ያውከቸው ፡ ጀመር ።
ክፉ ፡ የሆነ ፡ የምትሐቱ ፡ መልክ ፡ ፊቱ ፡ ያዘነ
ውን ፡ ሁሉ ፡ አጠፋ ።
፭ የእሳቱም ፡ ብርሃን ፡ አንዲት ፡ ሰዓት ፡ ያበራ ፡
ዘንድ ፡ አልቻለም ። ለዚች ፡ ሌሊት ፡ ጨለማ ፡
ሊያበሩ ፡ የተፈጠሩ ፡ የሚያበሩ ፡ ከዋክብትን ፡
ብርሃን ፡ ያበራ ፡ ዘንድ ፡ አልተቻለውም ።
፮ የሥራይ ፡ ሥራ ፡ የሚሆን ፡ የስንፍና ፡ ድካምን ፡
ባደረጉ ፡ ጊዜ ፡ ከሚታዩ ፡ ክስታና ፡ ከዶግ ፡ ተገ
ኝቶ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ከሚታይ ፡ እሳት ፡ ግር
ማው ፡ ፍጹም ፡ የሚሆን ፡ እሳት ፡ ድንገት ፡ ታያ
ቸው ፡ እንጂ ፡ የእሳት ፡ ብርሃን ፡ ያበራ ፡ ዘንድ ፡
አልቻለም ።
፯ ይኸውም ፡ በግብፃውያን ፡ ዘለፋ ፡ ሊሆንባቸው ፡
የወርቅ ፡ የብር ፡ ትዕቢት ፡ ነው ።
፰ በመከራ ፡ የተያዘች ፡ የሰውነት ፡ ድንጋጤዋን ፡
መታወኳን ፡ ያጠፉ ፡ ዘንድ ፡ ተስፋ ፡ የሰጡ ፡ እነ
ዚህን ፡ የሚያውክ ፡ ዘጠኙ ፡ መቅሠፍት ፡ ምን
ምን ፡ ባያስፈራቸው ፡ ዋዛ ፡ የሚሆን ፡ የትንኝ ፡
ማስፈራት ፡ አጥፍቷቸዋልና ።
፱ ከፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ በሚያንስ ፡ ከነፋስ ፡ የትነሣ ፡
ከሰው ፡ ፊት ፡ በሚበር ፡ በትንኝ ፡ አስወጥቶ ፡
ሰደዳቸው ፡ የደነገጡም ፡ ሆነው ፡ አሸሻቸው ።
በነፋስ ፡ አካል ፡ ከሰው ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ከሚሸሽ ፡
ከትንኙ ፡ የተነሣ ፡ መቆም ፡ አልተቻላቸውም ።
፲ ሥላሴ ፡ ምስክር ፡ የሚሆኑበት ፡ በሱ ፡ ላይ ፡ የሚ
ፈርዱበት ፡ የክፉ ፡ ፈርዖን ፡ ሥራው ፡ ዓመፅ ፡
ነውና ። ሁልጊዜ ፡ እሱ ፡ ከሙሴ ፡ ትእዛዝን ፡
ይቀበላል ፡ ለልቡናው ፡ እየታወቀው ፡ ዕው
ቀት ፡ ባለው ፡ ልቡናም ፡ እየተመለከተ ፡ ወዲ
ህም ፡ የጥመት ፡ የክፋት ፡ ሥራ ፡ ይሠራል ።
፲፩ በልቡናው ፡ በዚህ ፡ በሚያጠፋኝ ፡ በዚህ ፡ ያጠ
ፋኛል ፡ ብሎ ፡ መቅሠፍቱን ፡ ያሳስብ ፡ ነበር ፡
እንጂ ፡ ምንም ፡ ፍርሃት ፡ ያደረጉ ፡ አይደለምና ፡
የጥመት ፡ ሥራን ፡ ይሠራል ።
ጥቂት ፡ የልቡና ፡ ጥርጥር ፡ ቢኖርህ ፡ ባለማ ፲፪
ወቅ ፡ ነው ፡ በስንፍናም ፡ ነው ፡ ለፍርድም ፡
መንገድ ፡ የምትሰጥ ፡ ናት ፡ ተብላ ፡ ፈጽማ ፡
የምትታሰብ ፡ ነበረች ።
እርሷን ፡ መታገስ ፡ የማይቻል ፡ ከምታስጨንቅ ፡ ፲፫
ከሲኦል ፡ በውነት ፡ የወጣች ፡ ያች ፡ ሌሊት ፡
ከነርሱ ፡ በውነት ፡ የሸፈነቻቸው ፡ ጊዜ ፡ እር
ሷን ፡ ቀን ፡ ተኝተው ፡ ነበር ።
የሚያስደነግፁ ፡ አጋንንት ፡ አስደንግፁዋቸዋ ፲፬
ልና ። ምትሐቱን ፡ በማሳየት ፡ ያጥኗቸው ፡
አሉ ፡ የሰውነትንም ፡ አለኝታ ፡ የሚያደክም ፡
አለ ፡ ያላሰቡት ፡ ያልተጠራጠሩት ፡ ፍርሃት ፡
ድንጋጤ ፡ ድንገት ፡ ደረሰባቸው ።
በዚህ ፡ ያለው ፡ ማን ፡ ማን ፡ የሆነው ፡ ሁሉ ፡ እን ፲፭
ዲህ ፡ ነው ፡ የተኛም ፡ ቢሆን ፡ በግር ፡ ብረት ፡
ታሥሮ ፡ በሥር ፡ ቤት ፡ የሚጠበቅም ፡ ቢሆን ፡
ያለ ፡ እግር ፡ ብረት ፡ የሚጠበቅም ፡ ቢሆን ።
አራሽም ፡ ቢሆን ፡ እረኛም ፡ ቢሆን ፡ ምድርን ፡ ፲፮
በማረስ ፡ የሚደክም ፡ ምንደኛም ፡ ቢሆን ፡ በም
ድረ ፡ በዳ ፡ ተቀምጦ ።
በሌሊት ፡ ጨለማ ፡ ወገናቸው ፡ ሁሉ ፡ ስለታ ፲፯
ሠረ ፡ ፍጻሜ ፡ የሌላት ፡ የተገናኘችው ፡ የምታ
ስጨንቅ ፡ ያችን ፡ መከራ ፡ ታግሷልና ፡ በዚያ ፡
ያለው ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ማን ፡ ማን ፡ የሆነው ፡ ሰው ፡
እንዲህ ፡ ነው ፡ ያገኛቸውም ፡ ምትሐት ፡ እን
ዲህ ፡ ነው ፡ የሚያኳጭ ፡ ምትሐት ፡ ነው ፡ ከሚ
ጋርዱ ፡ ጭፍቅ ፡ ካሉ ፡ ከዛፎች ፡ የተነሣ ፡
ድምጡ ፡ ያማረ ፡ የጫሮች ፡ ቃል ፡ ነው ። ዜማ
ቸው ፡ ካማረ ፡ ከወፎች ፡ ድምጥ ፡ የተነሣ ፡ ነው ።
ገንትቶ ፡ የሚሔድ ፡ የውኃ ፡ ሻሻቴ ፡ ድምጥም ፡ ፲፰
ነው ፡ በማስፈራት ፡ የሚገለባበጡ ፡ የዋሻዎች ፡
ድምጥም ፡ ነው ፡ የሚሮጡ ፡ ሩጫቸውም ፡ የማ
ይታይ ፡ የከብቶች ፡ ሩጫ ፡ ነው ። በሚያስፈራ ፡
በታላቅ ፡ ቃል ፡ የሚጮሁ ፡ የአውሬዎችም ፡
ቃል ፡ ነው ፡ ከአውሬዎችና ፡ ከአዕዋፍ ፡ ቃል ፡
የተነሣ ፡ አስበሳቸው ፡ ድምጥን ፡ ለዋውጠው ፡
የሚመልሱ ፡ የሚያስፈሩ ፡ የተራራዎችም ፡
ድምጥ ፡ ነው ። አስደንግጦ ፡ ያጠፋቸው ፡ መከራ ፡
እንዲህ ፡ ነው ።
ዓለሙ ፡ ሁሉ ፡ በሚያበራ ፡ ብርሃን ፡ ያበራ ፡ ነበ ፲፱
ረና ፡ ያለ ፡ መከልከልና ፡ ያለበዘን ፡ ሥራውን ፡
ይጨርስ ፡ ነበርና ።
እነዚህን ፡ ግን ፡ ብቻቸውን ፡ ያገኛቸው ፡ ዘንድ ፡ ፳
ያለው ፡ የገሃነም ፡ ጨለማ ፡ ምሳሌ ፡ የሚሆን ፡
የጸና ፡ የሌሊት ፡ ጨለማ ፡ ጠወራቸው ፡ እነር
ሱም ፡ ለራሳቸው ፡ ከጨለማ ፡ የሚጸኑ ፡ ናቸው ።

ምዕራፍ ፡ ፲፰ ።

በወዳጆችህ ፡ በእስራኤል ፡ ዘንድ ፡ ግን ፡ ፩
ደገኛ ፡ ብርሃን ፡ ይበራ ፡ ነበር ፡ እነዚያ ፡ ሁሉ ፡
ቃላቸውን ፡ ይሰሙ ፡ ነበር ፡ መልካቸውን ፡
ግን ፡ አያዩም ፡ ነበር ።
እነዚያ ፡ የሚወዷቸው ፡ እስራኤልን ፡ ይደበድ ፪

ቧቸው ፡ ነበርና ። የተበደሉ ፡ እስራኤልንም ፡
መከራ ፡ ስለ ፡ አጸኑባቸው ፡ እስበሳቸው ፡ ይመ
ሰጋገኑ ፡ ነበር ።
፫፤ እሊህ ፡ ግን ፡ በተላከላቸው ፡ ለሚያድን ፡ ስጦታ ፡
ደስ ፡ አላቸው ፡ የማይታወቅ ፡ ጕዳናን ፡ ይመራ
ቸው ፡ ዘንድ ፡ የእሳት ፡ ምሰሶ ፡ ዋጋቸውን ፡
ሰጣቸው ።
፬፤ በሚወደድ ፡ መንገድም ፡ የሚበራ ፡ ፀሐይን ፡
ሰጣቸው ። የማይጠፋ ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ይሰጥ ፡
ዘንድ ፡ ያለው ፡ የሕግህ ፡ ዋጋህ ፡ ያላቸው ፡ ልጆ
ችህ ፡ እስራኤልን ፡ አሥረው ፡ አግዘዋቸዋልና ፡
ብርሃንን ፡ ያጡ ፡ ዘንድ ፡ በጨለማም ፡ ይታሠሩ ፡
ዘንድ ፡ ለኒህ ፡ ለግብፃውያን ፡ ግን ፡ ይገባቸ
ዋል ።
፭፤ የደጋጎች ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ይገድሉ ፡
ዘንድ ፡ በሰቡ ፡ በመከሩ ፡ ጊዜ ፡ ለዘለፋ ፡ ሲሆን
ባቸው ፡ አንዱ ፡ ልጅ ፡ ወድቆ ፡ ዳነ ። ብዙ ፡
ልጆቻቸውን ፡ በዚህ ፡ በሙሴ ፡ አጠፋህ ፡ ወገና
ቸውን ፡ ሁሉ ፡ በሰፊ ፡ ውኃ ፡ አጠፋህ ።
፮፤ የተማማሉባትን ፡ መሐላ ፡ ከወቁ ፡ በኋላ ፡ ይቺን ፡
በፍቅር ፡ ያስቧት ፡ ዘንድ ፡ አባቶቻችን ፡ ያቺን ፡
ሌሊት ፡ አወቋት ።
፯፤ ለወገኖችህ ፡ ለእስራኤል ፡ ድኅነትን ፡ አድርገህ ፡
እስራኤልን ፡ ለሚጣሉ ፡ ለግብፃውያን ፡ ጥፋ
ትን ፡ አድርገህ ፡ ወገኖችህ ፡ እስራኤልን ፡ በረ
ድኤት ፡ ተቀበልካቸው ።
፰፤ እስራኤልን ፡ የሚጣሉ ፡ ግብፃውያንን ፡ እንዳ
ጠፋሀቸው ፡ በጠራኸን ፡ ጊዜ ፡ እንደዚሁ ፡ አከ
በርከን ።
፱፤ አገልጋዮችህ ፡ ደጋግ ፡ የሚሆኑ ፡ እስራኤል ፡
ያማረ ፡ የተወደደ ፡ መሥዋዕትን ፡ ይሠዉ ፡
ነበረና ፡ በመስማማት ፡ የጌትነትህን ፡ ሕግ ፡ በል
ቡናቸውም ፡ አሳድረዋልና ። በዚህ ፡ እምሳል ፡
ደጋጎች ፡ እስራኤል ፡ ተድላ ፡ ደስታውን ፡ ተቀ
በሉ ፡ መከራውን ፡ ግን ፡ ለሚገባቸው ፡ ለግብ
ፃውያን ፡ ሰጠህ ።
፲፤ አባቶቻችን ፡ ግን ፡ አንተን ፡ እያመሰገኑ ፡ ተድላ ፡
ደስታውን ፡ ይናገሩ ፡ ነበር ፡ ነገራቸው ፡ ሳይት
ባበር ፡ ከጠላቶች ፡ ልቅሶ ፡ ጩኸት ፡ ጋራ ፡ ቃላ
ቸው ፡ ይገናኝ ፡ ነበር ። ባሮችም ፡ ስለ ፡ ልጆቻ
ቸው ፡ የልጆቻቸውን ፡ ድምፅ ፡ ያደምጡ ፡ ነበር ።
፲፩፤ የባሪያውም ፡ ቅጣት ፡ ከጌታው ፡ ጋራ ፡ በመቅ
ሠፍት ፡ ተካከለ ።
፲፪፤ ጭፍራውም ፡ ከንጉሡ ፡ ጋራ ፡ ይች ፡ መከራ ፡
የተካከለ ፡ ሆኖ ፡ አገኘቻቸው ። ሁሉም ፡ በአንድ
ነት ፡ በአንድ ፡ ምስል ፡ ሞቱ ። በአንዲት ፡
ሰዓት ፡ የከበረች ፡ ፍጥረታቸው ፡ ፈጽማ ፡ ጠፍ
ታለችና ፡ ደኅነኞች ፡ የሞቱትን ፡ ሰዎች ፡ ይቀብ
ሯቸው ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ አልተቻላቸው ፡ ቍጥር ፡
የሌላቸው ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ አስከሬኖች ፡ ነበሩ ።
፲፫፤ ስር ፡ ስለ ፡ ማሱ ፡ ቅጠል ፡ ስለበጠሱ ፡ ሁሉም ፡ የመ
ጣባቸውን ፡ መቅሠፍት ፡ አላወቁምና ፡ ግብፃው
ያን ፡ በበኵር ፡ ልጃቸው ፡ መጥፋት ፡ እስራኤል ፡
የእግዚአብሔር ፡ ልጆች ፡ እንደሆኑ ፡ አወቁ ።
ሁሉን ፡ የምትገዛ ፡ ዝምታና ፡ ፀጥታ ፡ ዓለሙን ፡ ፲፬፤
ሁሉ ፡ በሸፈነችው ፡ ጊዜ ።
አሸናፊ ፡ አርበኛና ፡ ሁሉን ፡ የሚችል ፡ ተጋ ፲፭፤
ዳይ ፡ የሚሆን ፡ ቃልህ ፡ ያቺን ፡ ሌሊት ፡ ተበቅ
ለዋታልና ።
ያለማድላት ፡ ያጠፋቸው ፡ ዘንድ ፡ ትእዛዝህ ፡ ፲፮፤
የተሳለ ፡ ሰይፍን ፡ ታጥቆ ፡ ከሰማይ ፡ ወርዶ ፡
መንግሥት ፡ በላቸው ፡ በግብፃውያን ፡ መከ
ከል ፡ በቆመ ፡ ጊዜ ፡ ደዌያቸው ፡ ሁሉ ፡ ሞትን ፡
ተመላ ፡ ከሰማይ ፡ ወርዶ ፡ ተጫናቸው ፡ ከምድ
ርም ፡ አጠፋቸው ።
ክፉዎች ፡ በሆኑ ፡ በላሞች ፡ ምትሐት ፡ ያንጊዜ ፡ ፲፯፤
አወካቸው ፡ ያላሰቧት ፡ ድንጋፄም ፡ በላያቸው ፡
ሠለጠነችባቸው ።
ከነዚህ ፡ እኩሌታው ፡ የሞተ ፡ ሆኖ ፡ በሌላ ፡ ፲፰፤
ቦታ ፡ የሚወድቅ ፡ አለ ፡ የሚሞቱባትን ፡ ምክ
ንያት ፡ አስቀድሞ ፡ ገለጠላቸው ።
ክፉ ፡ ነገር ፡ ስለምንም ፡ እንዲያገኛቸው ፡ እን ፲፱፤
ዲያጠፋቸውም ፡ ባለማወቅ ፡ እንዳይሆኑ ፡ ያወ
ኳቸው ፡ ላሞች ፡ አስቀድመው ፡ ይህንን ፡ ነግረ
ዋቸዋልና ፡ ገለጹላቸው ።
ከእስራኤልም ፡ አስቀድሞ ፡ ለሞት ፡ የሚያበቃ ፡ ፳፤
መከራ ፡ ያገኛቸው ፡ አሉ ። በምድረ ፡ በዳ ፡ እን
ዲህ ፡ ሆነ ፡ መቅሠፍቱ ፡ ከነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ብዙ ፡
አጠፋ ።
ነውር ፡ የሌለበት ፡ ሰው ፡ አሮን ፡ ይኸውም ፡ ፳፩፤
ልመና ፡ የሚያደርግበት ፡ ዕጣን ፡ የሚያጥንበት ፡
የሚያገለግልበት ፡ ልብሰ ፡ መትከፍ ፡ ነው ፡
የሚዳ ፡ ዐብቱን ፡ ይዞ ፡ ፈጥኖ ፡ ተግቷልና ፡ ነገር ፡
ግን ፡ መዓቱ ፡ ብዙ ፡ ሀመን ፡ ኃጢአታቸውን ፡
ለማቃለል ፡ ባለሟልነትን ፡ አገኘ ፡ መዓቱን ፡
ተቀዋወመ ፡ መቅሠፍቱንም ፡ ጸጥ ፡ አደረገ ፡
በዚህ ፡ ያንተ ፡ መልክተኛ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ራሱን ፡
አስታወቀ ።
የሚያጠፋ ፡ የቸነፈሩን ፡ ወገን ፡ አሸነፈ ፡ ቃል ፡ ፳፪፤
ኪዳናቸውንና ፡ ያባቶቻቸውን ፡ መሐላ ፡ በማ
ሳሰብ ፡ በሚያጠፋ ፡ ቃልህ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ይኸ
ውን ፡ በሥጋዊ ፡ ኃይል ፡ በሚዳ ፡ ዐብት ፡ ሥራ ፡
አይደለም ።
ብዛታቸው ፡ የማይቆጠር ፡ የሞቱ ፡ ሰዎች ፡ እስ ፳፫፤
በሳቸው ፡ በወደቁ ፡ ጊዜ ፡ በበሽተኞቹና ፡ በደ
ኅነኞቹ ፡ መካከል ፡ ከቆመ ፡ በኋላ ፡ መዓቱ ፡ ጸጥ ፡
ብሏልና ፡ ይኸውም ፡ በሥጋዊ ፡ ኃይል ፡ በሚዳ ፡
ዐብት ፡ ሥራ ፡ አይደለም ።
ለደኅነኞች ፡ መንገድ ፡ ለየ ፡ የዓለሙ ፡ ክህነት ፡ ፳፬፤
በልብሱ ፡ ጫፍ ፡ ላይ ፡ አለና ፡ ባሕርይ ፡ ከሚ
ባል ፡ ዕንቍ ፡ የተቀረጸ ፡ የአበውም ፡ ስም ፡
በጫንቃው ፡ ላይ ፡ አለና ፡ ያንተም ፡ ስም ፡ በራሱ ፡
ኩፋት ፡ ላይ ፡ አለና ።
የሚያጠፉ ፡ ቸነፈሮች ፡ በዚህ ፡ ራቁ ፡ እነዚህም ፡ ፳፭፤
ሥራዎች ፡ አስፈሯቸው ፡ ነገር ፡ ግን ፡ መቅሠ
ፍቱ ፡ በበቃ ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲፱ ።

፩ ያለርኅራኄ፡ፈጽማ፡እስከታጠፉቸው፡ድረስ፡
እግዚአብሔርን ፡ በዘነጉ ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ ግን ፡
መዓትህ ፡ ጠና ። የሚደረግ ፡ ሥራቸውን ፡ አስ
ቀድመው ፡ አውቀዋልና ።
፪ በነዚያ ፡ ላይ ፡ ግን ፡ መዓትህ ፡ ጠናች ፡ እነዚያ ፡
ከመሔድ ፡ መልሰዋቸዋልና ፡ ዳግመኛም ፡ በች
ኩላ ፡ ሰደዋቸዋልና ። በተጸጸቱ ፡ ጊዜ ፡ በሩጫ ፡
ጠበጠቡ ፡ በፊታቸው ፡ ኤርትራ ፡ አለና ፡ ብለ
ውም ፡ ተከሏቸው ።
፫ ገና ፡ በልቅሶ ፡ ሳሉ ፡ በአስከሬኖቻቸው ፡ መቃ
ብር ፡ ላይ ፡ ሲያለቅሱ ፡ ሲጮሁ ፡ ልዩ ፡ የሆነ ፡
የስንፍና ፡ አሳብ ፡ ሰበቻቸዋልና ፡ ሊሄዱ ፡ ዘንድ ፡
ከነርሱ ፡ ዘንድ ፡ ማልደው ፡ አስወጥተው ፡ የሰ
ደዷቸውን ፡ እንደ ፡ ከበለሉ ፡ ሰዎች ፡ ይከተሏ
ቸው ፡ ዘንድ ፡ በመሮጥ ፡ ጠበጠቡ ።
፬ የተጋቧት ፡ የመከራ ፡ መጨረሻ ፡ ወደሚሆን ፡
ወደዚህ ፡ ሥራ ፡ ሳበቻቸው ፡ (ስጥመት ፡) ዝን
ጋኤ ፡ አሳታቸው ፡ ከሥሩ ፡ መቅሠፍቶች ፡ የጐ
ደለውን ፡ ይፈጽሙ ፡ ይሞሉ ፡ ዘንድ ፡ ያገኛቸ
ውን ፡ መከራ ፡ አላሰቡም ።
፭ ወገኖችህ ፡ ድንቅ ፡ መንገድን ፡ ሔዱ ፡ እነዚህ ፡
ግን ፡ ክፉ ፡ ሞትን ፡ አገኙ ።
፮ መላዋ ፡ ኤርትራ ፡ ከወገኖቿ ፡ ከማዕበሏና ፡ ከሞ
ገዷ ፡ ጋራ ፡ ያለክፋት ፡ በደኅንነት ፡ ልጆችህ ፡
እስራኤል ፡ ይጠበቁበት ፡ ዘንድ ፡ ወዲህ ፡ የታ
ዘዘችበትን ፡ ትእዛዝ ፡ ዳግመኛ ፡ እያገለገለች ፡
በሰብአ ፡ ትካት ፡ መቅሠፍት ፡ ተመስላለችና ፡
እሊህ ፡ ግን ፡ ልዩ ፡ ሞትን ፡ አገኙ ።
፯ ደመና ፡ እስራኤልን ፡ የምትጋርድ ፡ ሆነች ፡
ኤርትራ ፡ ከቀድሞዋ ፡ ይልቅ ፡ የረጋች ፡ ሆና ፡
ታየች ፡ የደረቀችቱም ፡ ምድር ፡ የሰፋች ፡ መስክ ፡
ሆና ፡ ታየች ፡ በኤርትራ ፡ መካከል ፡ ያለ ፡ መሰ
ናክል ፡ የሌለው ፡ መንገድ ፡ ታየ ።
፰ በከበረች ፡ ታላቅ ፡ በሆነች ፡ በሥልጣንህ ፡ ተሠ
ውረው ፡ ወገኖችህ ፡ ሁሉ ፡ በሔዱባት ፡ ጽኑ ፡
በሆነ ፡ ማዕበል ፡ መካከል ፡ የለመለመ ፡ መስክ ፡
ታየ ፡ አቤቱ ፡ ያዳንካቸው ፡ አንተን ፡ ሲያመሰግኑ ።
፱ እነዚያ ፡ እንደ ፡ ፈረሾች ፡ እንደ ፡ ጌኞች ፡ እየዘ
ለሉ ፡ አመስግነውሃልና ፡ ሥራቸውንም ፡ በማ
ማፀን ፡ አስበውሃልና ፡ ይህን ፡ ድንቅ ፡ ሥራህን ፡
በዩ ፡ ጊዜ ፡ ይቺን ፡ ሥልጣንህን ፡ አመስግናት ።
፲ አገራቸው ፡ የእንስሳ ፡ ፍጥረትን ፡ ታስገኝ ፡ ስለ ፡
ነበረ ፡ ፈንታ ፡ ተቈናጣጭ ፡ ዝንብን ፡ እንዴት ፡
አስገኘች ፡ ባሕርስ ፡ በሰፊ ፡ ውኃ ፡ ውስጥ ፡ ያለ ፡
ፍጥረትን ፡ ታስገኝ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ ፈንታ ፡ ተስ
በን ፡ እንዴት ፡ አስገኘች ።
፲፩ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ መናውን ፡ በመጉብኸቸው ፡ ጊዜ ፡
እንግዳ ፡ የሚሆን ፡ የአዕዋፍ ፡ ፍጥረትን ፡ አዩ ፡
የወደዱትን ፡ የተድላና ፡ የደስታን ፡ ምግብን ፡
በተመኙ ፡ በለመኑ ፡ ጊዜ ።
፲፪ ልቡናቸውን ፡ ለማረጋጋት ፡ ከባሕር ፡ ውስጥ ፡
ብዙ ፡ ድርጭት ፡ ወጣላቸው ፡ ከመብረቆች ፡
ያራቀች ፡ አስቀድሞ ፡ በተደረገው ፡ በዘጠኙ ፡
መቅሠፍት ፡ ሠራዊት ፡ የምትመስል ፡ መቅሠ
ፍት ፡ በግብፃውያን ፡ ላይ ፡ መጣች ።
ነገር ፡ ግን ፡ ይኸውም ፡ ክፉ ፡ ነው ፡ እንግዳ ፡ መጥላ ፲፫
ትን ፡ ፈጽመው ፡ ስለ ፡ ወደዱ ፡ በክፋታቸው ፡ እን
ደሚገባ ፡ እነዚያ ፡ በውነት ፡ ተፈርዶባቸዋልና ፡
በግብፃውያን ፡ መቅሠፍት ፡ መጣችባቸው ።
ከሩቅ ፡ አገር ፡ በደረሱ ፡ ጊዜ ፡ እሊህ ፡ እስራኤል ፡
ግን ፡ የማያውቋቸው ፡ የገባያንን ፡ ሰዎች ፡ ተቀ
በሉ ። በጎ ፡ ነገር ፡ ሊያደርጉላቸው ፡ ሲጠቅማ
ቸው ፡ ከነሱ ፡ ዘንድ ፡ እንግዳ ፡ የሆኑ ፡ እስራኤልን ፡
እኒያ ፡ ግብፃውያን ፡ ግን ፡ በጭንቅ ፡ ገዟቸው ።
በሥራቸው ፡ መጐብኛ ፡ መመርመሪያ ፡ ይሆና ፲፬
ቸው ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የተፈረደባቸው ፡
በዚህ ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፡ ከነሱ ፡ ዘንድ ፡ እን
ግዳ ፡ የሆኑ ፡ እስራኤልን ፡ ግብፃውያን ፡ በጭ
ንቅ ፡ ተቀብለዋቸዋልና ።
እሊህ ፡ እስራኤል ፡ ግን ፡ ደጋግነት ፡ ካላቸው ፡ ፲፭
ከእስራኤል ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ የሆኑ ፡ የገባያንን ፡
ሰዎች ፡ በክብር ፡ ተቀበሉ ።
በብዙ ፡ ጭንቅ ፡ መከራን ፡ በጸኑባቸው ፡ ጊዜ ፡ ፲፮
ከደጋጎች ፡ ደጃፍ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ተሰበሰቡ ፡
እንደነዚያ ፡ ሰዎች ፡ ብርሃን ፡ በማጣት ፡ ጠፉ ፡
በጥልቅ ፡ ጨለማ ፡ ድንገት ፡ ተግዘዋልና ፡ ከነዚ
ያም ፡ አንዱም ፡ አንዱም ፡ ሁሉ ፡ የቤቱን ፡ የደጃ
ፉን ፡ መግቢያ ፡ መንገድ ፡ ይፈልግ ፡ ነበር ።
ፀሐይ ፡ ጨረቃ ፡ ከባሕርያቸው ፡ ተለውጠውብ ፲፯
ቸው ፡ ነበርና ። የዜማውን ፡ ነገር ፡ በማወቅ ፡
የበገና ፡ ስም ፡ እንዲለወጥ ፡ የቃና ፡ ሆኖ ፡ እን
ዲህ ፡ ጸንቶ ፡ እንዲኖር ፡ በማየት ፡ ፈጽሞ ፡ የሚ
ሰፈር ፡ ሥራ ፡ በየወገናቸው ፡ የተፈጠሩ ፡ ፀሐይ ፡
ጨረቃ ፡ ተለውጠውባቸዋልና ፡ አንዱም ፡ አን
ዱም ፡ ይፈልግ ፡ ነበር ።
በደረቅ ፡ ያሉ ፡ ፍጥረቶች ፡ ወደ ፡ ውኃ ፡ ተመ ፲፰
ልሰዋልና ፡ (ግብፃውያን ፡) በውኃ ፡ የሚኖሩ ፡
የሚዋኙ ፡ የተሳቦዎች ፡ አነዋወር ፡ ወደ ፡ ምድር ፡
ተመልሷልና ፡ አንዱም ፡ አንዱም ፡ የደጃፉን ፡
መግቢያ ፡ መንገድ ፡ ይፈልግ ፡ ነበር ።
እሳቱም ፡ በውኃው ፡ ውስጥ ፡ ፈጽሞ ፡ በረታ ፡ ፲፱
ውኃውም ፡ የባሕርዩን ፡ ፍጥረት ፡ ሠወረ ።
ፈጥኖ ፡ የሚጠፉ ፡ የእሳቱም ፡ ሙቀት ፡ ሥራው ፡ ፳
በይደለ ፡ በውኖች ፡ መካከል ፡ ወዲያ ወዲህ ፡
እያለ ፡ እየተመላለሰ ፡ የከብቶችን ፡ ሥጋ አላ
ቃጠለም ። የማይጠፉ ፡ የፍጥረት ፡ ወገን ፡ እሳ
ትም ፡ ፈጥኖ ፡ የሚጠፉ ፡ ውርጭንም ፡ አላቀለ
ጠውም ። በሥራው ፡ ሁሉ ፡ ከቤቱ ፡ የወገኖች
ህን ፡ ፈጽመህ ፡ ክብር ፡ አብዝተሃልና ። በሁሉ ፡
አክብረሃቸዋልና ፡ ወደኛ ፡ የመጣውን ፡ ነገር ፡
ሁሉ ፡ ቸርነትህን ፡ አላራቅህብንም ፡ እኛንም ፡
በየጊዜው ፡ ቸል ፡ አላልከንም ፡ በየቦታው ፡
ሁሉ ፡ አንተ ፡ ትኖራለህ ።

ለእግዚአብሔር ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ምስጋና ፡ ይግ
ባውና ፡ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ የዳዊት ፡ ልጅ ፡
ሰሎሞን ፡ የተናገረው ፡ ጥበብ ፡ መላ ፡ ተፈጸመ ።





# የሦስቱ ልጆች መዝሙር

፩ በጉድጓድ ፡ እሳት ፡ መካከልም ፡ ተመላለሱ ፡ እግ
ዚአብሔርንም ፡ ፈጽመው ፡ አመሰገኑት ።
፪ አዛርያም ፡ በእሳቱ ፡ መካከል ፡ ቁሞ ፡ እንዲህ ፡
ብሎ ፡ ጸለየ ÷ በእሳቱም ፡ መካከል ፡ ምስጋናን ፡
ጀመረ ፡—
፫ የአባቶቻችን ፡ ፈጣሪ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይክበር ፡
ይመስገን ÷ ስምህም ፡ ለዘላለም ፡ የተመሰገነ ፡
የከበረ ፡ ነው ፡ አለ ።
፬ በመጣህብን ፡ መከራ ፡ ሁሉ ፡ አንተ ፡ ጻድቅ ፡
ነህና ፤ ሥራህ ፡ ሁሉ ፡ የታመነ ፡ ነው ÷ ሥርዓ
ትህም ፡ ሁሉ ፡ የቀና ፡ ነው ÷ ፍርድህም ፡ ሁሉ ፡
እውነት ፡ ነው ።
፭ ባደረግህብን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ፍት ፡ ርት ፡ አደረ
ግህ ፤ በእውነተኛ ፡ ፍርድህ ፡ ስለ ፡ ኃጢአታ
ችን ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ መከራ ፡ አምጥተህብናልና ፡
በከበረች ፡ በአባቶቻችን ፡ አገር ፡ በኢየሩሳሌ
ምም ፡ ፍት ፡ ርት ፡ አደረግህ ። የተውንህ ፡ እኛ ፡
በድለናል ፤ ስተናልና ፡ በሁሉ ፡ በደልን ፤ ትእዛ
ዝህንም ፡ አልሰማንም ፤
፮ በጎ ፡ ረድኤት ፡ ይደረግልን ፡ ዘንድ ፡ እንዳዘዝ
ኸን ፡ ሕግህን ፡ አልጠበቅንም ÷ ትእዛዝህንም ፡
አላደረግንም ።
፯ ያመጣህብንን ፡ ያደረግህብንን ፡ መከራ ፡ ሁሉ ፡
በእውነተኛ ፡ ፍርድህ ፡ አደረግህብን ።
፰ ኃጢአተኞች ፡ ወንጀለኞች ፡ በሚሆኑ ÷ ከአ
ንተ ፡ ፈጽመው ፡ በራቁ ፡ በጠላቶቻችን ፡ እጅ ፡
ጣልኸን ፤ ከሰው ፡ ሁሉ ፡ ዓመፀኛ ፡ ክፉ ፡ በሆነ ፡
በብልጣሶርም ፡ እጅ ፡ አሳልፈህ ፡ ጣልኸን ።
፱ አሁንም ፡ አፋችንን ፡ ከፍተን ፡ እናመሰግን ፡
ዘንድ ፡ አገባባችን ፡ አይደለም ፡ በምንፈራህ ፡
በኛ ፡ በባሪያዎችህ ፡ የተደረገብንን ፡ ጕስቍል
ናችንና ፡ ኃፍረታችንን ፡ አይተህ ።
፲ ስሜ ፡ ይቅር ፡ ባይ ፡ ነው ፡ ስላልህ ፡ ፈጽመህ ፡
ለመከራ ፡ አትስጠን ፡ ቃል ፡ ኪዳንህንም ፡ አት
ለውጥብን ።
፲፩ ስለ ፡ በለምዋልህ ፡ ስለ ፡ ይስሐቅና ፡ ስለ ፡ ወዳ
ጅህ ፡ ስለ ፡ አብርሃም ፡ ስላከበርኸው ፡ ስለ ፡ ያዕ
ቆብም ፡ ቸርነትህን ፡ ከእኛ ፡ አታርቅ ፤
፲፪ እነርሱ ፡ ከአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ጥቂቶች ፡ ነበሩና ፡ ልጆ
ቻቸውን ፡ በባሕር ፡ ዳር ፡ እንዳለ ፡ አሸዋና ፡ እንደ ፡
ሰማይ ፡ ኮከብ ፡ ታበዛላቸው ፡ ዘንድ ፡ ታበዛላቸ
ዋለህ ።

ስለ ፡ ተናገርሃቸው ፡ ስለ ፡ እነዚህ ፡ ቸርነትህን ፡ ፲፫
ከእኛ ፡ አታርቅ ፡ ስለ ፡ ኃጢአታችን ፡ በሀገሩ ፡
ሁሉ ፡ ዛሬ ፡ የጐሰቈልን ፡ ሆን ።
በዚህ ፡ ወራት ፡ አለቃ ፡ የለም ፡ ነቢዩም ፡ የለም ፡ ፲፬
ንጉሡም ፡ የለም ፡ ቍርባንም ፡ መሥዋዕትም ፡
ዕጣን ፡ የሚያሸትቱ ፡ ካህናትም ፡ የሉም ፡ በየ
ዋህ ፡ ልቡና ፡ በቀና ፡ ሰውነት ፡ ተቀበልልን ፡
እንጂ ፤ ይቅርታህን ፡ ያገኙ ፡ ዘንድ ፡ በፊትህ ፡ ፲፭
ሃይማኖት ፡ የሚያጸኑበት ፡ አገር ፡ የለም ።
የላሞችንና ፡ (ሙሴ ፡ አሮን ፡) የጊደሮችን ፡ ፲፮
(ዳዊት ፡ ሰሎሞን ፡) የሰቡ ፡ የበዙ ፡ በጎችንም ፡
(ኢዮስያስ ፡) መሥዋዕት ፡ እንደ ፡ ተቀበልህ ÷
መሥዋዕታችንም ፡ ዛሬ ፡ በፊትህ ፡ እንደዚያ ፡
ይሁን ። ያመኑብህ ፡ ሁሉ ፡ እንዳያፍሩ ፡ መሥ
ዋዕታችን ፡ በአንተ ፡ ዘንድ ፡ ፍጹም ፡ ይሁን ።
አሁንም ፡ በፍጹም ፡ ልቡናችን ፡ እናምንሃለን ፡ ፲፯
እንፈራሃለን ፡ አታሳፍረን ፡ እንጂ ፤ ገጽ ፡ ረድኤ
ትህንም ፡ እንፈልጋለን ።
ከቍጣ ፡ ወደ ፡ ምሕረት ፡ እንደ ፡ መመለስ ፡ ፲፰
መጠን ፡ ይቅርታህን ፡ አድርግልን ፡ እንደ ፡ ቸር
ነትህም ፡ ብዛት ፡ በታምራትህ ፡ ከመከራው ፡
አድነን ፤ አቤቱ ÷ ለስምህ ፡ ምስጋናን ፡ ስጥ ።
በኛ ፡ በባሪያዎችህ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ የሚያደርጉ ፡ ፲፱
ሁሉ ፡ ይፈሩ ፡ በቀማቸውም ፡ ሁሉ ፡ ይጐስ
ቍሉ ፡ ኃይላቸውም ፡ ይድከም ፤
በዓለሙ ፡ ሁሉና ፡ ለሀገሩ ፡ ሁሉ ፡ የተመሰገንህ ፡ ፳
ፈጣሪ ፡ አንተ ፡ ብቻ ፡ እንደ ፡ ሆንህ ፡ ይወቁ ፡
አለ ።
እነዚያም ፡ ብላቴናዎች ፡ በንጉሥ ፡ ዘንድ ፡ ፳፩
ነገር ፡ ሠርተው ፡ ማጣላታቸውን ፡ አልተዉም ፡
በእሳቱም ፡ ድኚ ፡ አደሮማር ፡ የወይን ፡ አረግ ፡
ቍልቋል ፡ ቅንጭብ ፡ የባሕር ፡ አረፋ ፡ ጨመሩ ።
ነበልባሉም ፡ ከጕድጓድ ፡ አርባ ፡ ዘጠኝ ፡ ክንድ ፡ ፳፪
ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለ ።
እሳቱም ፡ እየተመላለሰ ፡ በከለዳውያን ፡ ምድጃ ፡ ፳፫
(ጕድጓድ ፡) አጠገብ ፡ ያገኘውን ፡ ሁሉ ፡ ያቃ
ጥል ፡ ነበር ።
እግዚአብሔር ፡ የላከው ፡ መልአክም ፡ ከአናን ፳፬
ያና ፡ ከአዛርያ ፡ ከሚሳኤልም ፡ ጋር ፡ ወደሚነ
ደው ፡ ወደ ፡ እሳቱ ፡ ምድጃ ፡ ወርዶ ፡ በጕድ
ጓድ ፡ ያለውን ፡ እሳት ፡ መታው ÷
የእሳቱንም ፡ ነበልባል ፡ እንደ ፡ ቀዘቀዘ ፡ ነፋስ ፡ ፳፭

፲፱፡ በአርባ፡ሰባተኛው፡ ኢዮቤልዩ፡ በሰባተኛው፡
ሱባዔ፡በሰባተኛው፡ዓመት፡አባትህ፡ከከነዓን፡
መጣ፥ በአርባ፡ስምንተኛው፡ ኢዮቤልዩ፡በአ
ራተኛው፡ሱባዔ፡በስድስተኛው፡ዓመት፡ተወ
ለድህ ፡ ይኸውም፡በእስራኤል፡ልጆች፡ላይ፡
መከራ፡የጸናበት፡ወራት፡ነው ።
፳፡ የግብጽ ፡ ንጉሥ ፡ ፈርዖንም፡የተወለደውን፡
ወንድ ፡ ወንዱን ፡ ልጆቻቸውን፡ሁሉ፡ወደ፡
ባሕር ፡ ይጥሉ ፡ ዘንድ ፡ በእነርሱ፡ላይ፡ትእዛ
ዝን፡አዘዘ ።
፳፩፡ አንተ፡እስክትወለድ፡ድረስ፡ሰባት፡ወር፡ልጆ
ቻቸውን፡ሲጥሉ፡ኖሩ።እናትህም፡ሦስት፡ወር፡
ሸሸገችህ ፨ ለእርስዋም፡ነገሩአት ። ሣጥን፡አሠ
ራችልህ፤ አደሮ፡ ማር ፡ የባሕር ፡ አረፋ ፡ ለበ
ጠቻት ፤ በወንዙ ፡ ዳር፡ በሣር፡ ፊላ፡ ቅጠል፡
ውስጥ ፡ አኖረቻት ። በውስጥዋ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡
አኖረችህ፤ እናትህም፡ ሌሊት፡ ሌሊት፡ እየመ
ጣች ፡ ታጠባህ፡ ነበር ፥ እኅትህ ፡ ማርያምም ፡
ቀን፡ቀን፡ከአሞራዎች፡ትጠብቅህ፡ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፰ ።

፩፡ በዚያ፡ወራት፡የፈርዖን፡ልጅ፡ተርሙት፡
በፈሳሽ ፡ ውኃ ፡ ትታጠብ ፡ ዘንድ ፡ ወጣች ።
ስታለቅስ፡ቃልህን፡ሰምታ፡ያመጡህ፡ዘንድ፡
ደንገጡሮችዋን፡ አዘዘች ። ወደ፡ እርስዋም ፡
አመጡህ፤ከሣጥንም፡አወጣችህ፤ራራችልህ ፨
፪፡ እኅትህም ፡— ከዕብራውያን ፡ ወገን ፡ ይህን፡
ሕፃን ፡ አጥብታ ፡ የምታሳድገው ፡ ሞግዚት ፡
ሄጄ፡ልጥራልሽን ? አለቻት ። ሄዳ፡እናትህን፡
ጠራቻት ፤ ደመወዝዋን ፡ ሰጠቻት ፥ አሳደገ
ችህም ።
፫፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በደግህ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ፈርዖን፡
ቤት ፡ ወሰዱህ ። ልጁ ፡ ሆንኸው ። አባትህም፡
ዕብራን፡መጽሐፍን፡አስተማረህ ።
፬፡ ሦስቱን፡ ሱባዔ ፡ ከፈጸምህ፡ በኋላ፡ ወደ፡ ቤተ፡
መንግሥት ፡ አገባህ፤ ከቤተ ፡ መንግሥት ፡ እስ
ክምትወጣበት፡ወራት፡ድረስ፡ሦስት፡የዘመን፡
ሱባዔ ፡ በቤተ ፡ መንግሥት ፡ኖርህ ። ከእስራ
ኤል ፡ ልጆች ፡ ወገን ፡ የሚሆን ፡ ዕብራዊን፡
ሲደበድበው ፡ ግብጻዊን ፡ አየኸው ፤ ገድለህ፡
በአሸዋ ፡ መካከል ፡ ቀበርኸው ።
፭፡ በሁለተኛው ፡ ቀን ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡
ወገን ፡ የሚሆኑ ፡ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ ሲጣሉ ፡ አገ
ኘህ ። በደለኛውን ፡ አይተህ ፡— ወንድምህን፡
ለምን ፡ ትመታዋለህ ? አልኸው ። ፈጽሞ ፡
ተቆጣ ፡— በእኛ ፡ ላይ ፡ ዳኛ ፡ አለቃ ፡ አድርጎ፡
የሾመህ ፡ ማን ፡ነው ? ወይስ ፡ ትላንትና ፡ ግብጻ
ዊን ፡ እንደ ፡ ገደልኸው ፡ ትገድለኝ ፡ ዘንድ ፡
ትወዳለህን ? አለህ ።
፮፡ ከዚህ፡ነገር፡መገለጥ፡የተነሣ፡ፈርተህ፡ሸሽህ ፨
፯፡ በአርባ፡ዘጠኝኛው፡ኢዮቤልዩ፡በሦስተኛው፡
ሱባዔ፡በስድስተኛው፡ዓመት፡ወደዚያ፡ሄደህ፡
ስድስት ፡ ሱባዔ ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ ተቀመጥህ ፨
በዳግመኛው ፡ ሱባዔ ፡ በሁለተኛው ፡ ዓመት ፡
ወደ ፡ ግብጽ ፡ ተመለስህ ፤ ይኸውም ፡ ሃምሳ ፡
ኢዮቤልዩ ፡ ነው ።
በደብረ ፡ ሲና ፡ የተናገረህን ፡ አንተ ፡ ታውቃ ፰፡
ለህ ። ለኃጢአት ፡ ምክንያት ፡ ሰውን ፡ ሁሉ ፡
የሚገዛ ፡ ዲያብሎስ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ምን ፡ ያደ
ርግ ፡ ዘንድ ፡ ወደደ ? ወደ ፡ ግብጽ ፡ በተመለስህ ፡
ጊዜ ፡ በጐዳና ፡ በጥላ ፡ በሚያደርጉት ፡ በዓል ፡
ቀን ፡ በፍጹም ፡ ኃይሉ ፡ ይገድልህ ፡ ዘንድ ፡ የወ
ደደ ፡ አይደለምን ?
በግብጻውያን ፡ በቀልንና ፡ ፍርድን ፡ ታደርግ ፡ ፱፡
ዘንድ ፡ እንደ ፡ ተላክህ ፡ በየ ፡ ጊዜ ፡ ግብጻውያ
ንን ፡ ከእጅህ ፡ ያድናቸው ፡ ዘንድ ፡ የወደደ ፡
አይደለምን ? ከእጁ ፡ አዳንሁህ ፤ በግብጽ ፡ በፈ
ርዖንና ፡ በቤተ ፡ ሰቡ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፥ በሕዝቡ ፡
ላይና ፡ በባሪያዎቹ ፡ ላይ ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ፡
በተላክህ ፡ ገንዘብ ፡ ድንቅ ፡ ተአምራትን ፡ አደ
ረግህ ፨
እግዚአብሔርም ፡ ስለ ፡ እስራኤል ፡ በእነርሱ ፡ ፲፡
ጽኑ ፡ በቀልን ፡ አደረገ ። በኀጒንቸርና ፡ በደም ፥
በውሻ ፡ ዝንብና ፡ በትንኝ ፥ ክፉ ፡ ቍስል ፡ በሆነ ፡
በሚፈላ ፡ ደዌ ፡ ሥጋ ፡ ፈጽሞ ፡ አጠፋቸው ።
ከብቶቻቸውን ፡ በዕብነ ፡ በረድና ፡ በሞት ፡ ፲፩፡
አጠፋ ፥ አዝመራቸውንም ፡ በዚህ ፡ ሁሉ ፡
አጠፋ ። ከበረድ ፡ የቀረውን ፡ በሚበላ ፡ በአን
በጣ ፥ በጨለማ ፥ በከብቱና ፡ በሰውም ፡ የበ
ኵር ፡ ልጅ ፥ በጣዖቶቻቸውም ፡ ሁሉ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ በቀልን ፡ አደረገ ። በእሳትም ፡ አቃ
ጠላቸው ፤ ሳይደረግ ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ፡ ሁሉ ፡
በአንተ ፡ ሥልጣን ፡ ተላከ ።
የግብጽንም ፡ ንጉሥ ፡ በሕዝቡ ፡ ፊትና ፡ በአገ ፲፪፡
ልጋዮቹ ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡ ስትናገረው ፡ ኖርህ ።
ሁሉም ፡ በቃልህ ፡ ተደረገ ። ታላላቆችና ፡ ክፉ
ዎች ፡ የሚሆኑ ፡ አሥሩ ፡ መቅሠፍቶች ፡ ለእስ
ራኤል ፡ በቀልን ፡ ትመልስበት ፡ ዘንድ ፡ በግ
ብጽ ፡ አገር ፡ መጡ ። እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ እስ
ራኤል ፡ ሁሉን ፡ አደረገ ፨ በግፍ ፡ እንደ ፡ ገዙአ
ቸው ፡ በእነዚያ ፡ ላይ ፡ በቀልን ፡ ይመልስ ፡
ዘንድ ፡ ከአብርሃም ፡ ጋር ፡ መሐላን ፡ እንደ ፡
ተማማለበት ፡ ፈቃዱ ፡ አደረገ ፨
ለኃጢአት ፡ ምክንያት ፡ ሁሉን ፡ አስቶ ፡ የሚ ፲፫፡
ገዛ ፡ ሰይጣን ፡ በፊትህ ፡ ይከራከርህ ፡ ነበር ፥
በፈርዖንም ፡ እጅ ፡ ይጥልህ ፡ ዘንድ ፡ ይወድ ፡
ነበር ፥ የግብጽንም ፡ ሰዎች ፡ በምዋርታቸው ፡
ይረዳቸው ፡ ነበር ። እስራኤልን ፡ ግን ፡ ይጠላ
ቸው ፡ ነበር ። በፊትህ ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ ይሠሩ ፡
ነበር ። በፊትህ ፡ ክፉ ፡ ሥራን ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡
ተውናቸው ፥ ድኅነት ፡ ግን ፡ በእጃቸው ፡ ይደ
ረግ ፡ ዘንድ ፡ አላሰናበትናቸውም ። እግዚአብ
ሔር ፡ በክፉ ፡ ቍስል ፡ አጠፋቸው ፤ አንድ ፡
ተአምራትን ፡ስንኳ ፡ ከማድረግ ፡ ምንም ፡ ምን ፡
አሳጥተናቸዋልና ፡ መከልከል ፡ ተሳናቸው ።
ግብጻውያን ፡ በሠራዊቶቻቸው ፡ ሁሉ ፡ በፈረ ፲፬፡
ሶቻቸውና ፡ በሰረገላዎቻቸው ፡ በግብጽ ፡ ሠራ
ዊት ፡ ሁሉ ፡ ብዛት ፡ ከአንተ ፡ በኋላ ፡ ይከለክሉ

አቸው ፡ ዘንድ ፡ እስኪበረታ ፥ ለግብጻውያንም ፡
እስኪያሰማቸው ፡ ድረስ ፡ ደርሶ ፥ በኀጢአት ፡
ምክንያት ፡ ሁሉን ፡ የሚገዛ ፡ ሰይጣን ፡ በተአም
ራቱ ፡ ሁሉ ፡ አልፈራም ።
፲፫፤ በግብጻውያንና ፡ በአንተ ፡ መካከል ፡ በእስራኤ
ልም ፡ መካከል ፡ ቆምሁ ። እስራኤልን ፡ ከሠራ
ራዊቱና ፡ ከእነርሱ ፡ እጅ ፡ አዳናቸው ።
፲፬፤ እግዚአብሔር ፡ በባሕር ፡ መካከል ፡ በደረቅ ፡
እንደ ፡ መሄድ ፡ አሻገራቸው ። እስራኤልን ፡
ይከተሉ ፡ ዘንድ ፡ ያወጣቸውን ፡ ወገኖች ፡ ሁሉ ፡
የግብጽ ፡ ሰዎች ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ በባ
ሕር ፡ እንደ ፡ ጣሉ ፥ አምላካችን ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ በባሕር ፡ መካከል ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡
በኋላ ፡ በወንዙ ፡ ጥልቅ ፡ ጣላቸው ። ብዙ ፡ በቀ
ልን ፡ ተበቀላቸው ። ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ወገን ፡
በፈሳሽ ፡ መካከል ፡ ስለ ፡ ጣሉት ፡ ስለሚጠባ ፡
ስለ ፡ አንዱ ፡ ልጅ ፡ ፋንታ ፡ ሺህ ፡ የሚሆኑ ፡
አርበኞች ፡ በሦስት ፡ ወገንም ፡ የሚመከከቱ ፡
ሰዎች ፡ ጠፉ ።
፲፭፤ በአሥራ ፡ አራተኛውና ፡ በአሥራ ፡ አምስተ
ኛው ፥ በአሥራ ፡ ስድስተኛውና ፡ በአሥራ ፡ ሰባ
ተኛው ፥ በአሥራ ፡ ስምንተኛውም ፡ ቀን ፡ በኃ
ጢአት ፡ ምክንያት ፡ ሰውን ፡ አስቶ ፡ የሚገዛ ፡
ሰይጣን ፡ እንዳይጣላቸው ፡ ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡
በኋላ ፡ ታስሮ ፡ ተግዞ ፡ ነበር ።
፲፮፤ በአሥራ ፡ ዘጠኝኛው ፡ ቀን ፡ ግን ፡ የግብጽን ፡
ሰዎች ፡ ይረዱአቸው ፡ ዘንድ ፡ የእስራኤልንም ፡
ልጆች ፡ ይከተሉ ፡ ዘንድ ፡ አሰናበታቸው ። ልቡ
ናቸውንም ፡ አጸና ፤ አበረታቸው ፤ ግብጻውያ
ንን ፡ ያጠፋቸው ፡ ዘንድ ፥ በባሕርም ፡ መካከል ፡
ይጥላቸው ፡ ዘንድ ፡ ከአምላካችን ፡ ከእግዚአ
ብሔር ፡ ዘንድ ፡ ታዘው ፡ ተበረታቱ ።
፲፱፤ ከግብጽ ፡ ሰዎች ፡ ልብስንና ፡ ገንዘብን ፥ የወር
ቁን ፡ መሣሪያና ፡ የብሩን ፡ መሣሪያ ፥ የእነርሱ
ንም ፡ መሣሪያ ፡ በሚዋሱበት ፡ ቀን ፡ የእስራኤ
ልን ፡ ልጆች ፡ እንዳይጣላቸው ፥ በግፍ ፡ ስለ ፡ ገዙ
አቸው ፡ ፋንታ ፡ ይማርኩአቸው ፡ ዘንድ ፡ በአ
ሥራ ፡ አራተኛው ፡ ቀን ፡ አሰርነው ። የእስራኤ
ልን ፡ ልጆች ፡ ከግብጽ ፡ በዶአቸውን ፡ አላወጣ
ናቸውም ።
፳፤ መጀመሪያው ፡ ወር ፡ በባተ ፡ በአሥራ ፡ አራተ
ኛው ፡ ቀን ፡ ገና ፡ ሳይመሽ ፡ ትሠዋው ፡ ዘንድ ፥
በአሥራ ፡ አምስተኛውም ፡ ቀን ፡ ማታ ፡ ፀሐይ ፡
ከሚገባበት ፡ ጊዜ ፡ ጀምሮ ፡ ሌሊት ፡ ይበሉት ፡
ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ስለ ፡ ፋሲካው ፡ ያዘዘ
ህን ፡ ትእዛዝ ፡ አስብ ፤ ይህች ፡ ሌሊት ፡ የበዓል ፡
መጀመሪያ ፡ ናትና ፥ የመሥዋዕትዋም ፡ መጀ
መሪያ ፡ ናትና ፡ አስብ ።
፳፩፤ እናንተም ፡ በግብጽ ፡ የፋሲካ ፡ በዓል ፡ አድርጋ
ችሁ ፡ ትበሉ ፡ ዘንድ ፡ ትቀመጣላችሁ ፤ የዲያ
ብሎስ ፡ ሠራዊት ፡ ሁሉ ፡ በግብጽ ፡ አገር ፡ ከፈ
ርዖን ፡ በኵር ፡ ልጅ ፡ ጀምሮ ፡ ተማርካ ፡ ሄዳ ፡
በወፍጮ ፡ሥር ፡ ሆና ፡ እስከምታገለግል ፡ ባሪያ ፡
ድረስ ፡ የበኵር ፡ ልጁን ፡ ይገድል ፡ ዘንድ ፡ ከብ
ቱንም ፡ ሁሉ ፡ ያጠፋ ፡ ዘንድ ፡ ተላከ ።
እግዚአብሔር ፡ የሰጣቸው ፡ ምልክት ፡ ይህች ፡ ፳፪፤
ናት ፤ በበሩ ፡ የደም ፡ ምልክት ፡ አለና ፡ በቤት ፡
ያሉ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ይድኑ ፡ ዘንድ ፡ ሠራዊቱ ፡
አልፈው ፡ ይሄዳሉ ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ የሆነውን ፡
የበግ ፡ ደም ፡ በቤቱ ፡ በር ፡ ወዳዩበት ፡ ቤት ፡
ለመግደል ፡ እንዳይገቡ ፡ የሰጣቸው ፡ ምልክት ፡
ይህች ፡ ናት ።
የእግዚአብሔር ፡ ሠራዊት ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብ ፳፫፤
ሔር ፡ እንዳዘዛቸው ፡ መጠን ፡ ሁሉን ፡ አደረጉ ።
ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ አልፈው ፡ ሄዱ ።
ከከብት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ሰው ፡ ድረስ ፡ እስከ ፡
ውሻም ፡ ድረስ ፡ ከእነርሱ ፡ ሰውን ፡ ሁሉ ፡ ለማ
ጥፋት ፡ መቅሠፍት ፡ ወደ ፡ እስራኤል ፡ አልገ
ባም ።
መቅሠፍቱ ፡ በግብጽ ፡ እጅግ ፡ ጽኑ ፡ ሆነ ፤ በግ ፳፬፤
ብጽ ፡ በውስጥዋ ፡ በድን ፡ የሌለበት ፡ ቤት ፡ አል
ነበረም ፤ እስራኤል ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ ለፋሲካው ፡
የታረደውን ፡ ሥጋ ፡ እየበላ ፡ ወይኑንም ፡ እየ
ጠጣ ፡ የአባቶቹን ፡ ፈጣሪ ፡ እግዚአብሔርን ፡
ፈጽሞ ፡ ያመሰግን ፡ ነበር ። ከጽኑ ፡ አገዛዝ ፥
ከፉ ፡ ከምትሆን ፡ ከግብጽም ፡ ለመውጣት ፡ የተ
ዘጋጀ ፡ ይሆን ፡ ነበር ።
አንተም ፡ ባለ ፡ በዘመንህ ፡ ሁሉ ፡ ይህችን ፡ ቀን ፡ ፳፭፤
አስብ ፤ ከአንዱ ፡ ዘመን ፡ እስከ ፡ አንዱ ፡ ዘመን ፡
በሕይወት ፡ በኖርህበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡
ሥርዓቱ ፡ ዓመት ፡ በዓመት ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ አድ
ርጋት ።
የዘላለም ፡ ሥርዓት ፡ ነውና ፡ ከቀን ፡ ቀን ፡ ከወር ፡ ፳፮፤
ወር ፡ አታስተላልፍ ። በየዓመቱ ፡ ሁሉ ፡ ከዓ
መት ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ በየትውልዳቸው ፡ ሁሉ ፡
ዕለቱን ፡ በዓል ፡ ያደርጉት ፡ ዘንድ ፡ በእስራኤል ፡
ልጆች ፡ ላይ ፡ ሥርዓት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በሰማይ ፡
ጽላት ፡ ታውቆአል ። የዘላለም ፡ ሥርዓት ፡ ነውና ፡
የተወሰነ ፡ ዘመን ፡ የለውም ።
ሰው ፡ ንጹሕ ፡ ሆኖ ፡ ሳለ ፡ በጊዜው ፡ ጊዜ ፡ ዕለ ፳፯፤
ቱን ፡ ያደርገው ፡ ዘንድ ፡ በዓሉ ፡ በሚከበርበት ፡
ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ ወዶ ፡ የሚቀበለውን ፡
ቍርባን ፡ ለማቅረብ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡
ለመብላትና ፡ ለመጠጣት ፡ ባይመጣ ፡ የእግዚአ
ብሔርን ፡ ቍርባን ፡ በየጊዜው ፡ ጊዜ ፡ አላቀረ
በምና ፡ ንጹሕ ፡ የሆነው ፥ አገሩም ፡ ቅርብ ፡ የሆ
ነው ፡ ያ ፡ ሰው ፡ ይጥፋ ። የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ መጥ
ተው ፡ በቀኑ ፡ ጊዜ ፡ በዓል ፡ የሚያደርጉ ፡ ይሆኑ ፡
ዘንድ ፡ ያ ፡ ሰው ፡ ለራሱ ፡ የኃጢአቱን ፡ ፍዳ ፡
ይቀበላል ። ቀኑ ፡ ሁለቱ ፡ እጅ ፡ ለብርሃን ፥ ሦስ
ተኛው ፡ እጅ ፡ ለጨለማ ፡ ተሰጥቶአልና ፡ መጀ
መሪያው ፡ ወር ፡ በባተ ፡ በአሥራ ፡ አራተኛው ፡
ቀን ፡ በምሽቱ ፡ መካከል ፡ ከቀኑ ፡ መጨረሻ ፡
ከሦስተኛው ፡ ሰዓት ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ሌሊቱ ፡
ሦስተኛ ፡ ሰዓት ፡ ድረስ ፡ ከቀኑ ፡ በሁለቱ ፡ እጅ ፡
በጊዜው ፡ ጊዜ ፡ በዓል ፡ ያድርጉ ።
በምሽቱ ፡ መካከል ፡ በዓል ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ፡ ፳፰፤
እግዚአብሔር ፡ ያዘዘው ፡ ሥርዓት ፡ ይህ ፡ ነው ።

የሚሠዋበትም ፡ በምሽቱ ፡ ፍጻሜ ፡ ጊዜ ፡
ይሁን ፡ እንጂ ፡ በብርሃኑ ፡ ጊዜ ፡ ሁሉ ፡ አይሁን ።
እስከ ፡ ሌሊቱ ፡ ማግሥት ፡ ድረስ ፡ ማታ ፡ ጊዜ ፡
ይብሉት ። ከሌሊቱ ፡ ማግሥት ÷ ከዚያም ፡ በኋላ ፡
የተረፈውን ፡ ሥጋ ፡ ሁሉ ፡ በእሳት ፡ ያቃጥሉት ።
፳፱ በእሳት ፡ አብስለው ፡ ጠብሰው ፡ ይብሉት ፡
እንጂ ፡ ቅቅሉን ፡ ብርንዶውን ፡ አይብሉት ።
ከእግሩና ፡ ከሆድ ፡ ዕቃው ፡ ጋር ፡ ራሱን ፡ በማ
ስተንተን ፡ ይጥበሱት ። ከእስራኤል ፡ ልጆች ፡
ምንምን ፡ የሚጠፋ ፡ ሰውነት ፡ የለምና ፡ ከእ
ርሱ ፡ ምንምን ፡ የሚሰበር ፡ አጥንት ፡ አይኑር ።
፴ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ በጊዜው ፡ ጊዜ ፡ ፋሲካን ፡ ያደ
ርጉ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ የእስራኤልን ፡
ልጆች ፡ አዘዛቸው ። ከእርሱም ፡ ምንምን ፡
አጥንትን ፡ መስበር ፡ አይኑር ። በዓል ፡ የሚያ
ደርግበት ፡ ቀን ፡ ናትና ÷ በዓል ፡ ሊያደርግበት ፡
የታዘዘችም ፡ ቀን ፡ ናትና ÷ በዓል ፡ የሚደረግ
በት ፡ ቀን ፡ ስለ ፡ ሆነች ፡ ከእርሱ ፡ ከቀን ፡ ወደ ፡
ቀን ፡ ከወር ፡ ወደ ፡ ወር ፡ መተላለፍ ፡ የለምና ።

ምዕራፍ ፡ ፶ ።

፩ አንተም ፡ የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ በዘመናቸ
ውና ፡ በየዓመቱም ፡ ሁሉ ፡ ከዓመት ፡ አንድ ፡
ቀን ፡ በጊዜው ፡ ፋሲካን ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡
እዘዛቸው ።
፪ የሚወደው ፡ መታሰቢያ ፡ ከእግዚአብሔር ፡
ፊት ፡ ይመጣል ። በሁሉ ፡ እንደ ፡ ታዘዘ ፡ በየ
ጊዜው ፡ በዓልን ፡ በደረጉ ፡ ጊዜ ፡ በዚያ ፡
ዘመን ፡ ፈጽሞ ፡ ለመጥፋት ፡ መቅሠፍት ፡ አይ
መጣባቸውም ።
፫ እግዚአብሔር ፡ በሚመሰገንበት ፡ በደብተራ ፡
ኦሪት ፡ አደባባይ ÷ በደብተራ ፡ ኦሪት ፡ አንጻ
ርም ፡ ቢሆን ፡ እንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ሊበሉት ፡
አይገባም ። በእስራኤል ፡ ወገኖች ፡ ሁሉ ፡ ፊት ፡
በጊዜው ፡ ጊዜ ፡ ያድርጉት ። የመጣ ፡ ሰው ፡
ሁሉ ፡ ፈጣሪያችሁ ፡ በሚመሰገንበት ፡ በደብ
ተራ ፡ ኦሪት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ዕለቱን ፡
ይብላው ፤ በእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ በደብ
ተራ ፡ ኦሪት ፡ ይበሉት ፡ ዘንድ ፡ እንደዚህ ፡ ተጽ
ፎአል ፡ ተሠርቶአልና ፡ ከሀያ ፡ ዘመን ፡ ጀምሮ ፡
ያለው ÷ ከዚያም ፡ በላይ ፡ ያለው ፡ አምላካችሁ ፡
እግዚአብሔር ፡ በሚመሰገንበት ፡ በደብተራ ፡
ኦሪት ፡ ዕለቱን ፡ ይብላው ።
፬ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ይዘዋት ፡ ወደሚኖሩ ፡
ወደ ፡ ከነዓን ፡ ከገቡ ፡ በኋላ ፡ እግዚአብሔር ፡
የሚመሰገንበት ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ በኢየሩሳ
ሌም ፡ እስኪሠራ ፡ ድረስ ፡ ሠራዊቶቻቸው ፡
ከያዙአቸው ፡ አገሮች ፡ አንዱ ፡ አገር ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ የሚመሰገንበትን ፡ ደብተራ ፡ ኦሪትን ፡
ይትከላሉ ።
፭ መጥተው ፡ በዓመት ፡ በዓመት ፡ እግዚአብሔር ፡
በሚመሰገንበት ፡ በደብተራ ፡ ኦሪት ፡ መካከል ፡
የፋሲካን ፡ በዓል ፡ የሚያደርጉ ፡ ይሁኑ ።
፮ በወረሱአት ፡ አገር ፡ ላይ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ስም ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ በተሠራበት ፡ ቀን ፡ ወደ
ዚያ ፡ ሄደው ፡ ፀሐይ ፡ ሲገባ ፡ ከቀኑ ፡ በሦስተ
ኛው ፡ ሰዓት ፡ ማታ ፡ ጊዜ ፡ በጉኑ ፡ የፋሲካውን ፡
በግ ፡ ይረዱ ፤ ደሙን ፡ በመሠዊያው ፡ ዙሪያ ፡
ይርጩት ። ስቡንም ፡ በመሠዊያው ፡ ባለ ፡ በእ
ሳቱ ፡ ላይ ፡ ያኑሩት ። ሥጋውንም ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ በሚመሰገንበት ፡ በደብተራ ፡ ኦሪት ፡ በእ
ግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በእሳት ፡ ጠብሰው ፡ ይብ
ሉት ።
በእግዚአብሔር ፡ ማደሪያ ፡ በደብተራ ፡ ኦሪት ፡ ፯
ነው ፡ እንጂ ÷ ያም ፡ ባይሆን ፡ ስሙ ፡ በሚጠራ
በት ፡ በሀገረ ፡ ምስካይ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በአገራ
ቸው ፡ በየአገሩም ፡ ሁሉ ፡ በዓል ፡ ማድረግ ፡
አይችሉም ፤ ከእግዚአብሔርም ፡ ሕግ ፡ ወጥ
ተው ፡ አይሳቱ ።
ሙሴ ! አንተም ፡ ዓመቱን ፡ በዓመት ፡ ቀኑን ፡ ፰
በቀን ፡ ታደርገው ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ታዘዘልህ ፡
የፋሲካውን ፡ ሥርዓት ፡ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ፡ የእ
ስራኤልን ፡ ልጆች ፡ እዘዛቸው ። በዓሉን ፡ ሊያ
ደርጉ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ቂጣ ፡ ይበሉ ፡ ዘንድ ፡
በቂጣ ፡ የሚከበረውንም ፡ እዘዛቸው ። ከግብጽ ፡
በወጣችሁ ፡ ጊዜ ፡ ኤርትራን ፡ ተሻግራችሁ ፡
ወደ ፡ ሱር ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ እስክትደርሱ ፡ ድረስ ፡
ይህችን ፡ በዓል ፡ በመቸከል ፡ አድርጋችኋታ
ልና ፡ በባሕርም ፡ ዳርቻ ፡ ላይ ፡ ፈጽማችኋታ
ልና ፡ መሥዋዕት ፡ በሚሠዋባቸው ፡ በእነዚህ ፡
በሰባቱ ፡ ቀኖች ፡ በአምላካችሁ ፡ መሠዊያ ፡ ላይ ፡
ዕለት ፡ ዕለት ፡ ቍርባኑን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡
ያቀርቡ ፡ ዘንድ ፡ እዘዛቸው ።
ከዚህም ፡ ሥርዓት ፡ በኋላ ፡ በሱባዔ ፡ የሚቈጠ ፱
ረውን ፡ ቀን ፡ በሲና ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ነገርሁህ ።
ይህችውም ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ በሲናና ፡ በኤሎም ፡
መካከል ፡ ያለች ፡ ናት ። የምድር ፡ ሰንበታትንም ፡
በደብረ ፡ ሲና ፡ ነገርሁህ ። በዓመቶች ፡ ሱባዔ ፡
ውስጥ ፡ በኢዮቤልዩ ፡ የሚቈጠሩ ፡ ዓመቶች
ንም ፡ ነገርሁህ ። ዓመቱን ፡ ግን ፡ ይዛችሁት ፡
ወደምትኖሩበት ፡ አገር ፡ እስክትገቡ ፡ ድረስ ፡
አልነገርንህም ። በእርስዋ ፡ ላይ ፡ በመኖራቸው ፡
ምድር ፡ ዕረፍትን ፡ ታድርግ ። በኢዮቤልዩ ፡
የሚቈጠረውንም ፡ ዘመን ፡ ያውቃሉ ።
ስለዚህም ፡ ነገር ፡ በዓመቶች ፡ የሚቈጠረውን ፡ ፲
ሱባዔ ፡ ሠራሁልህ ። አዳም ፡ ከተፈጠረ ፡ ጀምሮ ፡
እስከዚህች ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ያለው ፡ ዘመን ፡ አርባ ፡
ዘጠኝ ፡ ኢዮቤልዮታትና ፡ አንድ ፡ ሱባዔ ፡
ሁለት ፡ ዓመት ፡ ነው ። በምዕራብ ፡ በኩል ፡ ዮር
ዳኖስን ፡ ተሻግረው ፡ ወደ ፡ ምድረ ፡ ርስት ፡ ማዶ ፡
እስኪገቡ ፡ ድረስ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡
ለማወቅ ፡ ገና ፡ አርባ ፡ ዘመን ፡ ቀርቶአል ። እስ
ራኤል ፡ ከዘመኑ ፡ ሁሉ ÷ ከበደል ÷ ከጣዖት ÷
ከማይገባ ፡ ሥራ ÷ ከኃጢአት ÷ ከስሕተት ፡ እስ
ኪነጻ ፡ ድረስ ፡ ብዙ ፡ ኢዮቤልዮታት ፡ ያልፋሉ ።
በዓለሙም ፡ ሁሉ ፡ ተዘልሎ ፡ ይኖራል ፡ ማንም ፡ ፲፩
ማን ፡ ባለ ፡ ጋራ ፡ የለም ። ምንም ፡ ምን ፡ ክፉ ፡
ነገር ፡ የለበትም ። ምድርም ፡ ከዚያች ፡ ቀን ፡

ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዘመኑ ፡ ፍጻሜ ፡ ድረስ ፡ ከኃጢ
አት ፡ ትነጻለች ። በሱባዔ ፡ የሰንበታትንም ፡
ሥርዓት ፡ እነሆ ÷ ጻፍሁልህ ። የሥርዓቱንም ፡
ፍርድ ፡ ጻፍሁልህ ። በስድስቱ ፡ ቀኖች ፡ ሥራ
ህን ፡ ሥራ ።
፲፬፡ ሰባተኛይቱ ፡ ቀን ፡ ግን ፡ አምላካችሁ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ከመፍጠር ፡ ያረፈበት ፡ ቀን ፡ ናትና ፡
እናንተ ÷ ልጆቻችሁም ÷ ሴቶች ፡ ባሪያዎቻች
ሁና ፡ ወንዶች ፡ ባሪያዎቻችሁም ÷ ከብቶቻች
ሁም ፡ ሁሉ ÷ በአንተ ፡ ዘንድ ፡ የሚኖር ፡ መጻ
ተኛም ፡ ቢሆን ፡ ሥራውን ፡ ሁሉ ፡ አትሥሩ
ባት ። በዚያች ፡ ቀን ፡ ምንምን ፡ ሥራን ፡ የሚ
ሠራባት ፡ ሰው ፡ ይሙት ። ይህችን ፡ ቀን ፡ የሚ
ሽራት ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ከሚስቱም ፡ ጋር ፡ የሚገ
ናኝባትም ፡ ሰው ÷ ገሥግሦ ፡ ሄዶ ፡ ሥራን ፡
ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ ነገርን ፡ የሚነጋገርባት ፡ ሰው ፡
ሞትን ፡ ይሙት ።
፲፭፡ የሚሸጥባት ፡ የሚለውጥባትም ፡ ሰው ፡ ሁሉ ÷
ውኃንም ፡ የሚቀዳ ፡ ሰው ፡ በስድስተኛይቱ ፡
ቀን ፡ ያላዘጋጀ ፤ ከድንኳኑ ÷ ከቤቱም ፡ ያወጣ ፡
ዘንድ ፡ የሚሸከመውን ፡ ሸክም ፡ ሁሉ ፡ የሚያ
ነሣ ፡ ሰው ፡ ይሙት ።
፲፮፡ በስድስተኛው ፡ ቀን ፡ ያዘጋጃችሁትን ፡ በልታ
ችሁ ፡ ጠጥታችሁ ፡ ለማክበር ፡ በዚህች ፡ ቀን ፡
ከሥራው ፡ ሁሉ ፡ ዕረፉባት ፡ እንጂ ÷ በዓል ፡
የምታደርጉባትን ፡ ቀን ፡ የሰጣችሁ ፡ አምላካች
ሁን ፡ እግዚአብሔርንም ፡ አመስግኑባት ፡ እንጂ ፡
በሰባተኛይቱ ፡ ቀን ፡ ምንም ፡ ምን ፡ ሥራን ፡ አት
ሥሩ ። የከበረች ፡ ቀን ፡ ናት ÷ የመንግሥትም ፡
ቀን ፡ ናት ፤ በዘመናቸው ፡ በቀኑ ፡ ሁሉ ፡ ይህች ፡
ቀን ፡ ለእስራኤል ፡ ሁሉ ፡ የተቀደሰች ፡ ቀን ፡
ናት ።
፲፯፡ በዚህች ፡ የበዓል ፡ ቀን ፡ በልተው ፡ ጠጥተው ፡
ሊጠግቡባት ÷ በየቀኑ ፡ በየሱባዔው ፡ ዕጣንን ፡
ከማጠን ÷ ቍርባንን ፡ ከማቅረብ ÷ በእግዚአብ
ሔር ፡ ፊት ፡ መሥዋዕትን ፡ ከመሠዋት ፡ በቀር ፡
ሰው ፡ ከሚሠራው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ሊያርፉባት ፡
እግዚአብሔር ፡ ለእስራኤል ፡ የሰጠው ፡ ታላቅ ፡
ክብር ፡ ናትና ፡ አክብሩአት ።
አምላካችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሚመሰገንባት ፡ ፲፰፡
በደብተራ ፡ አሪት ፡ ቀዳሚ ፡ ቀዳሚ ፡ ይህ ፡ ሥራ ፡
ብቻ ፡ ይሠራ ። የእስራኤልን ፡ ልጆች ፡ ኃጢአት ፡
ያስተሰርዩ ፡ ዘንድ ÷ እግዚአብሔር ፡ ወድዶ ፡
ሊቀበለው ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ መታሰቢያ ፡ ሊሆን ፡
መባን ፡ ያቅርቡ ። እንደ ፡ ታዘዘው ፡ ለዘላለሙ ፡
ዕለት ፡ ዕለት ፡ ይቀበላቸዋል ።
ሥራን ፡ የሚሠራባት ፡ ሰው ፡ ሁሉ ÷ መንገድ ፲፱፡
ንም ፡ የሚሄድባት ፡ ሰው ÷ የሚያርስባት ፡ የሚ
ቆፍርባትም ፡ ሰው ÷ በቤቱም ፡ ቢሆን ፡ በቦታ
ውም ፡ ሁሉ ፡ ቢሆን ፡ መንጠር ፡ የሚያቃጥል
ባትም ፡ ሰው ÷ አህያና ፡ በቅሎ ፡ የሚጭንባት ፡
ሰው ÷ በፈረስና ፡ በበቅሎ ፡ ተቀምጦ ፡ የሚሄ
ድም ፡ ሰው ÷ በመርከብም ፡ ተጭኖ ፡ ወደ ፡
ባሕር ፡ የሚሄድ ፡ ሰው ÷
ማናቸውንም ፡ መትቶ ፡ የሚገድል ፡ ሰው ፡ ሁሉ ÷ ፳፡
ወፍንና ፡ እንስሳንም ፡ አድኖ ፡ የሚያርድባት ፡
ሰው ÷ አውሬም ፡ ቢሆን ፡ ወፍም ፡ ቢሆን ፡
ዓሣም ፡ ቢሆን ፡ አጥምዶ ፡ የያዘባት ፡ ሰው ÷
የሚጾምባትም ፡ ሰው ÷ ቅዳሚ ፡ ቀን ፡ ጠብን ፡
የሚያነሣ ፡ ሰው ÷ ቅዳሚ ፡ ቀን ፡ ከዚህ ፡ ሥር
ዓት ፡ ወጥቶ ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ ሥራ ፡ የሚሠራ ፡
ሰው ፡ ይሙት ።
የበዓሉን ፡ የቀኑን ፡ ሥርዓት ፡ በየዘመኑ ፡ አከፋ ፳፩፡
ፈል ፡ እጽፍልህ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእጄ ፡
በሰጠኝ ፡ በሰማይ ፡ ጽላት ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ÷
ምድር ፡ ዕረፍት ፡ እንደምታደርግበት ፡ ሥር
ዓት ÷ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ በዓልን ፡ የሚያደ
ርጉ ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ሥራን ፡ የሚሠራባት ፡
ሰው ፡ ሁሉ ፡ ይሙት ።
በኩፋሌ ፡ የተጻፈው ፡ ነገር ፡ በዚህ ፡ ተፈጸመ ።
ለእግዚአብሔር ፡ ምስጋና ፡ ይግባው ፡ ለዘላ
ለሙ ፡ አሜን ።

# መጽሐፈ ፡ ሄኖክ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

፩ ሕገ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የዘነጉ ፡ ሰዎችንና ፡
ክፉዎችን ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ለማራቅ ፡ መከራ ፡
በታዘዘበት ፡ ቀን ፡ ደጋግ ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ያላ
ቸው ፡ ጻድቃንና ፡ የተመረጡ ፡ ሰዎችን ፡ እን
ዳመሰገነ ፡ ሄኖክ ፡ ያመነበት ፡ ቃል ፡ ይህ ፡ ነው ።
፪ ሄኖክ ፡ ተናገረ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡ ዓይኑ ፡ ልቡናየ ፡
ተገልጦ ፡ ሳለ ፡ እውነተኛ ፡ ሰው ፡ የምሆን ፡
ጽድቁ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የተገኘልኝ ፡
እኔ ፡ ተናገርኩ ፡ በሰማይ ፡ ያሉ ፡ መላእክት ፡
ያሳዩኝ ፡ ሰኑሰ ፡ ራዕይን ፡ ከነሳቸው ፡ ዘንድ ፡ የሰ
ማሁትንም ፡ ሁሉ ፡ አየሁ ፡ እኔ ፡ ያየሁትም ፡
ራዕይ ፡ እንዳይቀር ፡ አወቅሁ ፡ አለ ።
፫ ይህም ፡ የሚደረገው ፡ በሦረኛው ፡ ትውልድ ፡
ነው ፡ እንጂ ፡ በሰባተኛው ፡ ትውልድ ፡ አይደ
ለም ።
፬ የደናግልን ፡ ነገር ፡ የሕጋውያንንም ፡ ነገር ፡ ከማ
ደሪያው ፡ ከወጣ ፡ ገናናና ፡ ሰኑ ፡ ከሆነ ፡ ከፈጣሪ ፡
ጋራ ፡ ተናገርኩ ።
፭ አራቱን ፡ ማዕዘነ ፡ ዓለም ፡ ከፈጠረ ፡ ከማደሪ
ያውም ፡ ወጥቶ ፡ ሕግ ፡ ለመሥራት ፡ በደብረ ፡
ሲና ፡ ከሚቆም ፡ ከሰማይም ፡ ወርዶ ፡ በእስራ
ኤል ፡ መካከል ፡ በከሃሊነቱ ፡ ከሚገለጥ ፤ ሁሉ ፡
ከሚፈራው ፡ ለምስጋና ፡ የሚተጉ ፡ መላእክ
ትም ፡ ከሚነዋወጡለት ፡ ከጽንፍ ፡ እስከ ፡ ጽንፍ ፡

ያሉ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ከሚፈሩት ፡ ሰኑ ፡ መንቀጥ
ቀጥም ፡ ከሚንቀጠቀጡለት ፡ ረዳጅዎች ፡ ተራ
ሮች ፡ ከሚደነግጡለት ÷ የሙሴ ፡ አሮንን ፡ ረዳ
ጅዎች ፡ ከረብታዎችም ፡ ከሚዋረዱለት ፡ (ሰበ ፡
ሊቃናት ፡) ሰምም ፡ ከእሳት ፡ የተነሣ ፡ እንዲቀ
ልጥ ÷ እንደዚያ ፡ ከሚቀልጡለት ፡ ምድርም ፡
በማየ ፡ አይኅ ፡ ከምትሰጥምለት ፡ በምድርም ፡
ያለ ፡ ሁሉ ፡ ከሚጠፉለት ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ ተነጋገ
ርሁ ።
፮፡ ፍርዱም ፡ በኃጥአን ፡ ሁሉ ፡ በጻድቃንም ፡ ላይ ፡
ሁሉ ፡ ይደረጋል ።
፯፡ ለወዳጆቹ ፡ ግን ፡ ፍቅር ፡ አንድነትን ፡ ያደርግላ
ቸዋል ፡ (ሕጋውያን ፡) የተመረጡ ፡ ሰዎችንም ፡
ይጠብቃቸዋል ፡ (ደናግል ፡) ለነሱም ፡ ይቅ
ርታ ፡ ይደረግላቸዋል ።
፰፡ ሁሉም ፡ የአምላክ ፡ ገንዘቦች ፡ ይሆናሉ ፡ በክብ
ርም ፡ ይከናወናሉ ፡ ይከብራሉ ፡ የአምላክ ፡ ብር
ሃንም ፡ ያበራላቸዋል ።
፱፡ ለወዳጆቹ ፡ ይፈርድላቸው ፡ ዘንድ ፡ እነሆ ፡
ከብዙ ፡ መላእክት ፡ ጋራ ፡ ይመጣል ፡ ሕገ ፡ እግ
ዚአብሔርንም ፡ የዘነጉ ፡ ሰዎች ፡ ያጠፉቸዋል ፤
ሕገ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የዘነጉ ፡ ሰዎችና ፡ ኃጥ
አን ፡ በሱ ፡ ፈጸመው ፡ ስለ ፡ አደረጉት ፡ ነገር ፡
ሁሉ ፡ ሥጋዊ ፡ ደማዊን ፡ ሁሉ ፡ ይወቅሳል ።
፲፡ በሰማይ ፡ የሚኖሩ ፡ ፀሐይ ፡ ጨረቃ ፡ ሥራቸ
ውን ፡ እንዳይለወጡ ፡ ሁሉም ፡ እንዲወጣ ፡
እንዲገባ ፡ በየዘመኑ ፡ ሁሉም ፡ እንደ ፡ ተሠራ ፡
ከዘዛቸውም ፡ ትእዛዛቸው ፡ እንዳይተላለፉ ፡
በሰማይ ፡ ያለውን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ አወቅሁ ፡
ተረዳሁ ።
፲፩፡ ምድርን ፡ እይዋት ፡ ከመጀመሪያው ፡ ጀምሮ ፡
እስከ ፡ መጨረሻው ፡ ድረስ ፡ በሷ ፡ ላይ ፡ ከሚሠ
ራው ፡ ሥራ ፡ የተነሣ ፡ የሚታይ ፡ የአምላክ ፡
ሥራው ፡ ሁሉ ፡ እንዳይለወጥ ፡ ልብ ፡ አድርጉ ።
፲፪፡ በጋውን ፡ ክረምቱን ፡ እዩት ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡
ውሀን ፡ እንደ ፡ ተመላች ፡ ደመናውም ፡ ጠዛ
ውም ፡ ዝናቡም ፡ በሷ ፡ ላይ ፡ አርፈውባት ፡
እንዲኖሩ ፡ እዩ ።
፲፫፡ ከብሉይ ፡ ክረምት ፡ ጀምሮ ፡ ከሦስት ፡ ወር ፡
ክረምት ፡ በኋላ ፡ እስከሚመጣ ፡ እስከ ፡ አዲስ ፡
በጋ ፡ ድረስ ፡ ከሚቆዩ ፡ ቅጠላቸው ፡ ከማይረ
ግፍ ፡ ከሥራ ፡ አራት ፡ እንጨቶች ፡ በቀር ፡ እን
ጨቶች ፡ ሁሉ ፡ ምጥጥ ፡ ድርቅ ፡ ብለው ፡ እን
ዳታዩ ፡ ቅጠላቸውም ፡ ሁሉ ፡ እንዲረግፍ ፡
አወቅሁ ፡ ተረዳሁ ።
፲፬፡ አስቀድሞ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ፀሐይ ፡ እንዲጸና ፡
ዳግመኛም ፡ የበጋውን ፡ ወራት ፡ ተረዳሁ ።
፲፭፡ እናንተ ፡ ግን ፡ የፀሐይ ፡ ዋዕይ ፡ ስለ ፡ ጸና ፡ የድ
ንኳን ፡ ጥላና ፡ የዛፍ ፡ ጥላን ፡ ትፈልጋላችሁ ፡
ምድርም ፡ ከዋዕዩ ፡ ጽናት ፡ የተነሣ ፡ ትቃጠላ
ለች ።
፲፮፡ እናንተ ፡ ግን ፡ ስለ ፡ ተቃጠለች ፡ ምድርን ፡ ድን
ጋይዋንም ፡ መርገጥ ፡ አትችሉም ።
፲፯፡ እንጨቶች ፡ ሁሉ ፡ በቅጠል ፡ ልምላሜ ፡ እንዲ
ሸፈኑ ፡ ኋላም ፡ እንዲያፈሩ ፡ አወቅሁ ።
ለዘላለሙ ፡ ሕያው ፡ ሆኖ ፡ የሚኖር ፡ እሱ ፡ እነ ፲፰፡
ዚህን ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ፈጠረላችሁ ፡ የነዚህን ፡
ሁሉ ፡ ነገር ፡ ፈጽማችሁ ፡ እወቁ ።
በያመቱ ፡ የሚሆነው ፡ ሥራውም ፡ በፊቱ ፡ ነው ፡ ፲፱፡
ፍጥረቱም ፡ ሁሉ ፡ ለሱ ፡ ይገዛሉ ፡ ፈጣሪ ፡ እንደ ፡
ሠራው ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ ሲደረግ ፡ ይኖራል ፡
እንጂ ፡ ከወሰነላቸው ፡ አይነዋወጡም ።
ፈሳሾችና ፡ ባሕሮችም ፡ አንድ ፡ ሆነው ፡ ሥራ ፳፡
ቸውን ፡ እንዲጨርሱ ፡ እወቁ ።
እናንተ ፡ ልበ ፡ ድንጋዮች ፡ ከሥራው ፡ ወጣ ፳፩፡
ችሁ ፡ እንጂ ፡ በገናንነቱ ፡ ላይ ፡ በረከሰች ፡ በና
ንተ ፡ አፍ ፡ ታላላቅ ፡ ጽኑ ፡ ሐሜትንም ፡ አማች
ሁት ፡ እንጂ ፡ እናንተ ፡ በሕጉ ፡ አልጸናችሁም ፡
የጌታችሁንም ፡ ትእዛዝ ፡ አላደረጋችሁም ።
ፍቅር ፡ አንድነት ፡ አታደረግላችሁም ፡ ስለዚህ ፡ ፳፪፡
ነገር ፡ እናንተም ፡ ዘመናችሁን ፡ ትረግማላችሁ ፡
በሕይወት ፡ የምትኖሩባቸውንም ፡ ዘመኖች ፡
ታጣላችሁ ፤ በናንተም ፡ የዘላለም ፡ መርገም ፡
ይበዛባችኋል ፡ ይቅርታም ፡ አይደረግላችሁም ።
በዘላለም ፡ መርገም ፡ ተይዛችሁ ፡ በዚያም ፡ ፳፫፡
ወራት ፡ የናንተን ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ለጻድቃን ፡
ሁሉ ፡ ትሰጣላችሁ ፡ ኃጥአን ፡ ደቂ ፡ መዘሙር
ዶቻችሁ ፡ ዘወትር ፡ እናንተን ፡ ይረግማሉ ፡
ከኃጥአን ፡ ደቂ ፡ መዘሙርዶቻችሁም ፡ ጋራ ፡
እናንተን ፡ መከራው ፡ አንድነት ፡ ያገኛችኋል ።
ለተመረጡ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ጸጋ ፡ ክብር ፡ ፍቅር ፡ ፳፬፡
አንድነትና ፡ ተድላ ፡ ደስታውም ፡ ይደረግላቸ
ዋል ፡ (ደናግል) ።
እነሱ ፡ ግን ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያትን ፡ ይወርሷ ፳፭፡
ታል ፡ ሕገ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለዘነጋችሁ ፡ በና
ንተስ ፡ መርገም ፡ ይሆንባችኋል ።
ለተመረጡም ፡ ሰዎች ፡ ጥበብ ፡ ቢሰጣቸው ፡ ፳፮፡
እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ ይድናሉ ፡ ጥበብ ፡ ያላቸው ፡
እነሱም ፡ ለሱ ፡ ይገዛሉ ፡ እንጂ ፡ በመዘንጋ
ትም ፡ ሆኖ ፡ በትቢትም ፡ ሆኖ ፡ ዳግመኛም ፡
አይበድሉም ።
ዳግመኛም ፡ አይበድሉም ፡ በሕይወት ፡ በሚኖ ፳፯፡
ሩበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ኃጢአት ፡ ሠርተው ፡
አይፈረድባቸውም ፡ በሕይወት ፡ የኖሩበትን ፡
ቍጥር ፡ ይጨርሳሉ ፡ እንጂ ፡ በመቅሠፍትና ፡
በመዓትም ፡ አይቀሠፉም ።
በሕይወት ፡ የሚኖሩበት ፡ ወራት ፡ በፍቅር ፡ ፳፰፡
አንድነት ፡ ይበዛል ፡ በተድላ ፡ በደስታ ፡ የሚኖ
ሩባቸውም ፡ ዘመኖች ፡ በሕይወታቸው ፡ በሚኖ
ሩበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ በተድላ ፡ በደስታ ፡ ለዘላ
ለም ፡ በሚሆን ፡ ፍቅር ፡ አንድነትም ፡ ይበዛሉ ።

## ምዕራፍ ፡ ፪ ።

የሰው ፡ ልጆች ፡ ከበዙ ፡ በኋላ ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ። ፩፡
በዚያ ፡ ወራትም ፡ መልከ ፡ መልካሞች ፡ ደመ ፡ ፪፡
ግቡዎች ፡ ልጆች ፡ ተወለዱላቸው ፡ በደብር ፡
ቅዱስ ፡ ያሉ ፡ ደቂቀ ፡ ሴትም ፡ እነሱን ፡ አይ
ተው ፡ ወደዱቸው ።

፫፡ እስበሳቸውም ፡ ኑ ፡ ለኛ ፡ ከቃየል ፡ ልጆች ፡
ሴቶችን ፡ እንምረጥ ፡ ለኛ ፡ ልጆችን ፡ እንው
ለድ ፡ አሉ ።
፬፡ አለቃቸው ፡ የሆነ ፡ ስማዝያ ፡ እኔስ ፡ ይህ ፡ ሥራ ፡
ይሠራ ፡ ዘንድ ፡ አትወዱም ፡ ብዬ ፡ እነሆ ፡ እፈ
ራለሁ ፡ የዚችም ፡ የዐናች ፡ ኃጢአት ፡ ፍዳ ፡
እምቀበል ፡ እኔ ፡ ብቻ ፡ እሆናለሁ ፡ አላቸው ።
፭፡ ይችን ፡ ምክር ፡ እንዳንለውጣት ፡ ይችንም ፡
ምክር ፡ ቁም ፡ ነገር ፡ እንድናደርጋት ፡ ሁላችን ፡
ተለያይተን ፡ እርስ ፡ በርሳችን ፡ ማላን ፡ እንማ
ማል ፡ ብለው ፡ ሁሉም ፡ መለሱለት ።
፮፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ ሁሉም ፡ አንድ ፡ ሆነው ፡ ሁሉም ፡
እርስ ፡ በርሳቸው ፡ ተለያይተው ፡ ማሉበት ፡
ሁሉም ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ሆኑ ።
፯፡ አርዳስ ፡ ወደሚባል ፡ በታም ፡ ወረዱ ፡ ይኸ
ውም ፡ የአርሞንኤም ፡ ተራራ ፡ ራስ ፡ ነው ፡
እርስበርሳቸው ፡ ተለያይተው ፡ ምለውበታልና ፡
የአርሞንኤምንም ፡ ተራራ ፡ በማላ ፡ ተራራ ፡
ብለው ፡ ጠሩት ።
፰፡ አለቆቻቸውም ፡ ስማቸው ፡ ይህ ፡ ነው ፡ መጀ
መሪያው ፡ አለቃቸው ፡ ስማዝያ ፡ ነው ፡ ሁለተ
ኛው ፡ ዑራኪበራምኤል ፡ ሦስተኛው ፡ አኪቢ
ኤል ፡ አራተኛው ፡ ጣምኤል ፡ አምስተኛው ፡
ራሙኤል ፡ ስድስተኛው ፡ ዳንኤል ፡ ሰባተ
ኛው ፡ ኢዜቃኤል ፡ ስምንተኛው ፡ ሱሩቃያል ፡
ዘጠኝኛው ፡ አስኤል ፡ አሥረኛው ፡ አርሞርስ ፡
አሥራ ፡ አንደኛው ፡ በጥርኤል ፡ አሥራ ፡ ሁለ
ተኛው ፡ አናንኤል ፡ አሥራ ፡ ሦስተኛው ፡
ዘቂቢ ፡ አሥራ ፡ አራተኛው ፡ ሳምሳፒኤል ፡
አሥራ ፡ አምስተኛው ፡ ስርትኤል ፡ አሥራ ፡ ስድ
ስተኛው ፡ ጡሩኤልዮም ፡ አሥራ ፡ ሰባተኛው ፡
ያኤል ፡ አሥራ ፡ ስምንተኛው ፡ አራዝያል ፡ ነው ፤
የሁለቱ ፡ መቶ ፡ አለቆች ፡ አለቆቻቸው ፡ እኒህ ፡
ናቸው ፡ ሌሎችም ፡ ሁሉ ፡ ከነሱ ፡ ጋራ ፡ አሉ ።
፱፡ ከነሳቸው ፡ ሚስት ፡ አገቡ ፡ ሁሉም ፡ ለየራሱ ፡
አንዳንዲቱን ፡ መረጠ ።
፲፡ ወደነሱም ፡ ይገቡ ፡ ዘንድ ፡ ጀመሩ ፡ ከነሱም ፡
ጋራ ፡ አንድ ፡ ሆኑ ፡ (ደረሱባቸው ።
፲፩፡ ሟርትን ፡ ምታት ፡ ማሳየትን ፡ አስተማሩዋቸው ፡
ሥር ፡ መማስን ፡ ቅጠል ፡ መበጠስንም ፡ አመለ
ከቷቸው ።
፲፪፡ እነሱም ፡ ፀንሰው ፡ ረጃጅሞች ፡ አርበኞች ፡ ልጆ
ችን ፡ ወለዱ ፡ ቁመታቸውም ፡ ሦስት ፡ ሦስት ፡
ሺህ ፡ ክንድ ፡ ነው ።
፲፫፡ አባት ፡ እናቶቻቸው ፡ እነሱን ፡ መመገብ ፡ እስ
ኪሳናቸው ፡ ድረስ ፡ ደርሰው ፡ እነዚህ ፡ ሰው ፡
የደከመበትን ፡ ገንዘብ ፡ ሁሉ ፡ በሉ ።
፲፬፡ ረጃጅሞቹም ፡ ልጆች ፡ አባት ፡ እናቶቻቸውን ፡
ይበሏቸው ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ መብላት ፡ ተመለሱ ።
፲፭፡ አውሬዎችንና ፡ ወፎችን ፡ ዓሣዎችንና ፡ ተሐዋ
ስያንንም ፡ እያመለኩ ፡ ይበድሉ ፡ ጀመር ።
፲፮፡ እርስ ፡ በርሳቸውም ፡ ሥጋቸውን ፡ ተባሉ ፡
ከሷም ፡ ደምን ፡ ጠጡ ።
፲፯፡ ያን ፡ ጊዜም ፡ ምድር ፡ በደለኞችን ፡ ከሰሰቻ
ቸው ፡ (ትሑታኑን ፡ ልዑላኑን) ።
አዛዝዔልም ፡ ለሰዎች ፡ ሾተልና ፡ ሰይፍ ፡ መሥ ፲፰፡
ራትን ፡ ጋሻ ፡ መሰንዶድንም ፡ ጥሩር ፡ መሥራ
ትንም ፡ አስተማራቸው ።
ከነሱ ፡ በታች ፡ የሚሆኑ ፡ ሥራቸውንም ፡ ሌላ ፡ ፲፱፡
ጌጽና ፡ አምባሮችን ፡ ቅንድብ ፡ መሸለልንና ፡
ዓይን ፡ መኳልን ፡ ከተመረጠና ፡ ከከበረ ፡ ዕንቍ ፡
ሁሉ ፡ የሚበልጥ ፡ ዕንቍንም ፡ እንዕስላ ፡ መሞ
ቅን ፡ ሁሉ ፡ የዓለምንም ፡ ለውጥ ፡ አሳይዋቸው ፡
(ፈረሱን ፡ በቅሎውን ፡ ሰው ፡ ማድረግ) ።
ዕኑ ፡ በደል ፡ ብዙ ፡ ሰሰንም ፡ ተደረገ ፤ ሳቱ ፡ ፳፡
ሰሰኑ ፡ ሥራቸውም ፡ ሁሉ ፡ ጠፋ ።
አሚዛራክ ፡ ጋኔን ፡ መሳብን ፡ ምታት ፡ ማሳየ ፳፩፡
ትን ፡ ሥር ፡ መማስን ፡ ቅጠል ፡ መበጠስንም ፡
ሁሉ ፡ አስተማረ ፡ አርማሮስም ፡ ጋኔን ፡ መሳ
ብን ፡ አስተማረ ።
በረቅእልም ፡ ኮከብ ፡ መቍጠርን ፡ አስተማረ ። ፳፪፡
ኮከብኤልም ፡ ምልክት ፡ ማሳየትን ፡ አስተማረ ። ፳፫፡
ጥሞኤልም ፡ ኮከብ ፡ መቍጠርን ፡ አስተማረ ። ፳፬፡
አስራድኤልም ፡ የጨረቃን ፡ አካሄድ ፡ አስተ ፳፭፡
ማረ ።
በሰዎችም ፡ ጥፋት ፡ ሰዎች ፡ ጮሁ ፡ ቃላቸውም ፡ ፳፮፡
ወደ ፡ ሰማይ ፡ ደረሰ ።
ያን ፡ ጊዜ ፡ ሚካኤልና ፡ ገብርኤል ፡ ሱርኤልና ፡ ፳፯፡
ሱርያል ፡ በሰማይ ፡ ሆነው ፡ ጐበኙ ።
በዚህ ፡ ዓለም ፡ በግፍ ፡ የፈሰሰ ፡ የብዙ ፡ ሰው ፡ ፳፰፡
ደምን ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ የሚሠራ ፡ ግፉን ፡ ሁሉ ፡
አዩ ።
እስበሳቸውም ፡ የሰዎችን ፡ የጩኸታቸውን ፡ ፳፱፡
ቃል ፡ ተናገሩ ። ምድርም ፡ ብቻዋን ፡ ቀርታ ፡
(ትሑታኑ ፡ ) ጩኸቷ ፡ ከሰማይ ፡ በር ፡ እስኪ
ደርስ ፡ ድረስ ፡ ጮኸች ።
አሁንም ፡ በሰማይ ፡ ያላችሁ ፡ መላእክት ፡ የሞቱ ፡ ፴፡
ሰዎችን ፡ ነፍሳት ፡ ልመናችንን ፡ ወደ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ አግቡልን ፡ እናንተን ፡ ይከሳሉ ፡ አሉ ።
ለነገሥ ፡ ንጉሣቸውን ፡ እንዲህ ፡ አሉት ፡ የጌ ፴፩፡
ቶች ፡ ጌታ ፡ አንተ ፡ ነህና ፡ ከምላኮች ፡ በላይ ፡
ያለህ ፡ አምላክም ፡ አንተ ፡ ነህና ፡ ከነገሥታ
ትም ፡ በላይ ፡ ያለህ ፡ ንጉሥ ፡ አንተ ፡ ነህና ።
የጌትነትህም ፡ ዙፋን ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ዘመን ፡ ፴፪፡
ጸንቶ ፡ ይኖራል ፡ ስምህም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡
ዘመን ፡ ለዘላለሙ ፡ የከበረ ፡ የተመሰገነ ፡ ነውና ፡
የከበርህ ፡ የተመሰገንህ ፡ ነህና ።
ሁሉንም ፡ የፈጠርህ ፡ አንተ ፡ ፈጥረህ ፡ የሁ ፴፫፡
ሉም ፡ ሥልጣን ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ ነውና ፡ (በጅህ)
በፊትህም ፡ ሁሉ ፡ የተገለጠ ፡ ነውና ።
አንተም ፡ ሁሉን ፡ መርምረህ ፡ ታውቃለህና ፡ ፴፬፡
ካንተም ፡ ሊሰወር ፡ የሚቻለው ፡ የለምና ።
አዛዝኤል ፡ ያደረገውን ፡ እይ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ፴፭፡
ግፉን ፡ ሁሉ ፡ እንዳስተማረ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡
የተሰወሩትን ፡ ሁሉ ፡ በሰማያት ፡ የሚሠሩትን ፡
እንዳስተማረ ፡ እያ ፡ አሉት ።
ከሱ ፡ ጋራ ፡ አንድነት ፡ ያሉትን ፡ ይገዛ ፡ ዘንድ ፡ ፴፮፡
አንተ ፡ ሥልጣንን ፡ የሰጠኸው ፡ ስማዝያም ፡

ምታት ፡ ማሳየትን ፡ እንዳስተማረ ፡ እይ ።
፴፯፤ አንድ ፡ ሁነውም ፡ ወደ ፡ ቃየል ፡ ልጆች ፡ ሄዱ ፤
በለዚህም ፡ ሴቶች ፡ ጋራ ፡ ደረሱባቸው ፡ ረከሱ ፡
እሊህንም ፡ ኃጢአቶች ፡ ገለጡላቸው ።
፴፰፤ ሴቶችም ፡ ረጃጅም ፡ ልጆችን ፡ ወለዱ ፡ በዚ
ህም ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ግፍንና ፡ ደምን ፡ ተመ
ላች ።
፴፱፤ አሁንም ፡ ከሥጋቸው ፡ የተለዩ ፡ ነፍሳት ፡ እነሆ ፡
ይጮሃሉ ፡ እስከ ፡ ሰማይ ፡ እስኪደርስ ፡ ድርስ ፡
ይከሳሉ ።
፵፡ ጩኸታቸውም ፡ እስከ ፡ ሰማይ ፡ ደረሰ ፡ በዚህ ፡
ዓለም ፡ የሚሠራው ፡ ግፍ ፡ ከመገለጡ ፡ የተነሣ ፡
መዳን ፡ አይችሉም ።
፵፩፤ ይህንንም ፡ ሳይደረግ ፡ አንተ ፡ ታውቀዋለህ ፡ ይህ
ንንም ፡ የባለጸጎችንና ፡ የድሆችንም ፡ ነገር ፡
አንተ ፡ ታውቀዋለህ ።
፵፪፤ የምትነግረንም ፡ ነገር ፡ የለም ፡ በዚህስ ፡ ነገር ፡
ምን ፡ እናደርጋቸው ፡ ዘንድ ፡ ይገባል ።

ምዕራፍ ፡ ፲ ።

፩፤ ያን ፡ጊዜም ፡ ልዑል ፡ ገናና ፡ የከበረ ፡ ፈጣሪ ፡
ተናገረ ፡ ወደ ፡ ላሜክ ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ ኖኅም ፡
ሱርያልን ፡ ላከው ።
፪፤ በኔ ፡ ስም ፡ አምነህ ፡ ራስህን ፡ ከማየ ፡ አይህ ፡
ሰውር ፡ በለው ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ትጠፋለችና ፡
የሚመጣ ፡ የመከራውን ፡ መጨረሻ ፡ግለጽለት ፡
አለው ።
፫፡ በዚችም ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ የጥፋት ፡ ውሀ ፡
ይመጣ ፡ ዘንድ ፡ አለው ፡ በውስጧም ፡ ያለው ፡
ሁሉ ፡ ይጠፋል ።
፬፤ አሁንም ፡ እሱ ፡ ይሸሽ ፡ ዘንድ ፡ ልጁም ፡ በዓ
ለሙ ፡ ሁሉ ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡ አስተምረው ፡
አለው ።
፭፡ ዳግመኛም ፡ እግዚአብሔር ፡ ሩፋኤልን ፡ አዛዝ
ኤልን ፡ እጁን ፡ እግሩን ፡ አስረህ ፡ በጨለማ ፡
ውስጥ ፡ አግዘው ።
፮፡ በዱዳኤል ፡ ያለች ፡ ምድረ ፡ በዳዋንም ፡ ክፈ
ታት ፡ እሱንም ፡ በዚያ ፡ በጨለማው ፡ ውስጥ ፡
ጣለው ፡ በላዩም ፡ እንክብል ፡ እንክብል ፡ ሻሮ ፡
ሻሮ ፡ ድንጋዮችን ፡ ግጠምበት ።
፯፤ ጨለማንም ፡ አልብሰው ፡ በዚያ ፡ ለዘላለሙ ፡
ይኑር ፤ ብርሃንን ፡ እንዳያይ ፡ ፍርድ ፡ በሚደረ
ግበት ፡ ዕለተ ፡ ምጽአት ፡ ወደ ፡ ገሃነም ፡ እንዲ
ሄድ ፡ ፊቱን ፡ በጨለማ ፡ሸፍነው ፡ አለው ።
፰፡ ደቂቀ ፡ ሴት ፡ ያጠፏት ፡ ምድርንም ፡ እንዳድ
ናት ፡ ምድርን ፡ እንዳነፃት ፡ የምድርንም ፡ ንጽ
ሕና ፡ ተናገር ።
፱፡ ለኃጢአት ፡ የሚተጉ ፡ ደቂቀ ፡ ሴት ፡ በገደሉ
በት ፡ ለልጆታቸውም ፡ በስተማሩት ፡ ኃጢአት ፡
ሁሉ ፡ ምሥጢር ፡ የሰው ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ አይ
ጠፉም ።
፲፤ በአዛዝኤል ፡ ሥራ ፡ ትምህርትም ፡ ምድር ፡
ሁሉ ፡ ጠፋች ፡ የሰውንም ፡ ሁሉ ፡ ኃጢአት ፡
በሱ ፡ጻፍበት ፡ አለው ።
ገብርኤልንም ፡ እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡ ተናቁ ፡ ፲፩፤
ሰዎችና ፡ ወዳመንዝራዎች ፡ ወደ ፡ ዘማም ፡
ልጆች ፡ ሂድ ፡ ያመንዝራይቱንም ፡ ልጆች ፡
ለኃጢአት ፡ የሚተጉ ፡ የሴትንም ፡ ልጆች ፡
ከሰው ፡ ለይተህ ፡ አጥፋቸው ፡ አለው ።
እስበሳቸው ፡ ተቀራደው ፡ ወደሚጠፉበት ፡ ፲፪፤
በታ ፡ አስወጥተህ ፡ ስደዳቸው ፡ የዘመን ፡ ርዝ
መት ፡ የላቸውምና ፡ እነሱ ፡ ራሳቸው ፡ በሰ
ይፍ ፡ ተቀራደው ፡ ያልቃሉ ።
የዘላለም ፡ ሕይወትን ፡ ሊኖሩ ፡ ተስፋ ፡ ያደርጋ ፲፫፤
ሉና ፡ ከነሱ ፡ አንዱም ፡ አንዱ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡
ዘመንን ፡ ሊኖር ፡ ይመስለኛልና ፡ ሁሉም ፡ ይለ
ምንሃል ፡ ላባቶቻቸው ፡ ለነሱም ፡ ፍቅር ፡ አን
ድነት ፡ አይደረግላቸውም ። ( አስታርቀን ፡
ብለው ፡ )
ሚካኤልንም ፡ እግዚአብሔር ፡ ሂደህ ፡ ለስም ፲፬፡
ያዛ ፡ ንገረው ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ ላሉ ፡ በኃጢአታ
ቸው ፡ ሁሉ ፡ ከለሳቸው ፡ ጋራ ፡ ይጠፉ ፡ ዘንድ ፡
ከሴቶችም ፡ ጋራ ፡ ለተባበሩ ፡ ሰዎች ፡ ንገራ
ቸው ፡ አለው ።
ልጆቻቸውም ፡ ተቀራደው ፡ ካለቁ ፡ በኋላ ፡ እነ ፲፭፡
ሱም ፡ የሚወዷቸው ፡ የልጆቻቸውን ፡ ጥፋት ፡
ካዩ ፡ በኋላ ፡ የጥፋታቸው ፡ መጨረሻና ፡ ፍር
ዳቸው ፡ እስከሚደረግበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ የዘ
ላለምም ፡ ፍርድ ፡ እስኪፈጸም ፡ ድረስ ፡ ሰባ
ውን ፡ ትውልድ ፡ በምድር ፡ ከረብታ ፡ በታች ፡
አሥረህ ፡ አግዛቸው ፡ አለው ።
በዚያም ፡ ወራት ፡ በጭንቅ ፡ ሊኖሩ ፡ በእሳቱ ፡ ፲፮፤
በታች ፡ ወዳለው ፡ በታ ፡ ይወስዷቸዋል ፡ በግ
ዞት ፡ ቤትም ፡ ለዘላለሙ ፡ ተዘግቶባቸው ፡ ይኖ
ራሉ ።
ያን ፡ ጊዜም ፡ ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዘላለሙ ፡ ፲፯፡
ድረስ ፡ መላከቸው ፡ አንድነት ፡ ይቃጠላል ፡
ይጠፋል ፡ እስከ ፡ ልጅ ፡ ልጅ ፡ ዘመን ፡ መጨ
ረሻ ፡ ድረስም ፡ ይጋዛሉ ።
ሰዎችን ፡ በድለዋቸዋልና ፡ ዋዛ ፡ የሚወዱ ፡ ፲፰፤
ሰዎችን ፡ ሁሉ ፡ ለኃጢአት ፡ የሚተጉ ፡ የደቂቀ ፡
ሴት ፡ ልጆችንም ፡ አጠፋቸው ፡ ግፉንም ፡ ሁሉ ፡
ከዚህ ፡ ዓለም ፡ አጥፋ ፡ ክፉ ፡ ሥራም ፡ ሁሉ ፡
ይጥፋ ፡ የቀና ፡ ሕግንና ፡ እውነት ፡ ሥራን ፡ የሚ
ሠራ ፡ ኖኅም ፡ ለዘላለሙ ፡ ይገለጥ ።
ሥራውም ፡ ሁሉ ፡ ለበረከት ፡ ይሆናል ፡ ሕጉጋ ፲፱፡
ቱም ፡ በተድላ ፡ በደስታ ፡ ይፀናሉ ።
አሁንም ፡ ደጋጎች ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአብ ፳፡
ሔር ፡ ይገዛሉ ፡ ሺህ ፡ ልጆችንም ፡ እስኪወ
ልዱ ፡ ድረስ ፡ ደኅነኞችን ፡ ይሆናሉ ። (ፍጹም ፡
ልጅ ፡)
የሕፃንነታቸውን ፡ የሽምግልናቸውንም ፡ ወራት ፡ ፳፩፤
ሁሉ ፡ በተድላ ፡ በደስታ ፡ ይጨርሳሉ ።
በነዚያም ፡ ወራቶች ፡ ምድር ፡ ሁሉ ፡ በውነት ፡ ፳፪፤
ትታረሳለች ፡ በሁለመናዋም ፡ እንጨቶችን ፡
ትተክላለች ፡ በረከትንም ፡ ትመላለች ።
ተድላ ፡ ደስታ ፡ ያለባቸው ፡ እንጨቶችም ፡ ፳፫፤
ሁሉ ፡ በሷ ፡ ላይ ፡ ይተከላሉ ፤ ወይኖችም ፡ በሷ ፡

ይተክላሉ ፡ በሷም ፡ ላይ ፡ የሚተከለው ፡ ወይን ፡ ሊያጠግብ ፡ ያፈራል ፡ በሷም ፡ የሚዘራው ፡ ዘር ፡ ሊያጠግብ ፡ ያፈሪ ኋ ።

፳፩ አንዲቱም ፡ መስፈሪያ ፡ ብዙ ፡ ፍሬ ፡ ታፈራለች ፡ አንዲቱም ፡ መስፈሪያ ፡ ዘይት ፡ አሥር ፡ የዘይት ፡ ዓውድማን ፡ ትመላለች ።

፳፪ አንተ ፡ ግን ፡ ምድርን ፡ ከግፉ ፡ ሁሉ ፡ ከበደሉም ፡ ሁሉ ፡ ከኀጢአቱም ፡ ሁሉ ፡ ከመበደልም ፡ ሁሉ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ከሚሠራው ፡ ሁሉ ፡ ከሚያንድፈው ፡ ጣዖትም ፡ ሁሉ ፡ አንፃት ።

፳፫ በዚህ ፡ ዓለም ፡ አጠፋቸው ፡ ከሰው ፡ የተወለዱ ፡ ልጆችም ፡ ሁሉ ፡ ደጋግ ፡ ሰዎችን ፡ ይሁኑ ፡ አሕዛብም ፡ ሁሉ ፡ እኔን ፡ የሚያመልኩ ፡ እኔን ፡ የሚያመሰግኑ ፡ ይሁኑ ።

፳፬ ሁሉም ፡ ለኔ ፡ ይሰግዳሉ ፡ ምድርም ፡ ከጥፋት ፡ ሁሉ ፡ ከሚሠራውም ፡ ኀጢአት ፡ ሁሉ ፡ ከተደረገበትም ፡ መቅሠፍት ፡ ሁሉ ፡ ጭንቅ ፡ መከራ ፡ ሁሉ ፡ ትነፃለች ።

፳፭ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ዘመን ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ድረስ ፡ በሷ ፡ ጥፋት ፡ አመጣበት ፡ ዘንድ ፡ ዳግመኛ ፡ አላመጣበትም ።

፳፱ በነዚያም ፡ ወራቶች ፡ በሰዎች ፡ ልጆች ፡ አገዛዛቸው ፡ ላይና ፡ በትክልታቸው ፡ ላይ ወደ ዚህ ፡ ዓለም ፡ ዝናሞችን ፡ አወርድላቸው ፡ ዘንድ ፡ በሰማዮች ፡ ያሉ ፡ በረከት ፡ የሚገኝባቸው ፡ ዳመናዎችን ፡ እከፍታለሁ ። (አዛለሁ ፡ )

፴ የቀና ፡ ነገርና ፡ ፍቅር ፡ አንድነት ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ወራት ፡ ሁሉ ፡ በልጅ ፡ ልጅም ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ አንድ ፡ ሁነው ፡ ይኖራሉ ።

ምዕራፍ ፡ ፬ ።

፩ ከነገር ፡ ሁሉ ፡ አስቀድሞ ፡ ሄኖክ ፡ ተሠወረ ።

፪ ከሰውም ፡ ልጆች ፡ በተሠወረበት ፡ በታ ፡ ሳለ ፡ የሚያውቀው ፡ አልነበረም ፡ ይሞት ፡ ይድንም ፡ የሚያውቅ ፡ የለም ።

፫ ሥራውም ፡ ሁሉ ፡ በተሠወረበት ፡ ወራት ፡ በቅዳሴያቸው ፡ ከሚተጉ ፡ መላእክት ፡ ጋራና ፡ ከቅዱሳን ፡ ጋራ ፡ ነበር ።

፬ እኔም ፡ ሄኖክ ፡ ገናና ፡ ጌታን ፡ ባራቱ ፡ ማዕዘነ ፡ ዓለም ፡ የነገሠ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰግነው ፡ ጀመር ።

፭ ሕግን ፡ በሰው ፡ ልቡና ፡ የምጽፍ ፡ እኔን ፡ ሄኖክንም ፡ ለቅዳሴያቸው ፡ የሚተጉ ፡ መላእክት ፡ እነሆ ፡ ይጠሩኛል ።

፮ ሕግን ፡ በልቡናህ ፡ የምትጽፍ ፡ ሄኖክ ፡ ለኀጢአት ፡ ለሚተጉ ፡ ሰማያዊ ፡ ማዕርጋቸውን ፡ የከበረ ፡ ዘላለም ፡ ጸንቶ ፡ የሚኖር ፡ መንግሥተ ፡ ሰማይንም ፡ አተው ።

፯ ከሴቶችም ፡ ጋራ ፡ ለጠፉ ፡ የቃየል ፡ ልጆችም ፡ እንደሚያደርጉ ፡ ላደረጉ ፡ ለደቂቀ ፡ ሴት ፡ ሂደህ ፡ ንገር ፡ አሉኝ ።

፰ ራሳቸው ፡ ሚስት ፡ አገቡ ፡ በዚህም ፡ ዓለም ፡ ታላቅ ፡ ጥፋትን ፡ ጠፉ ።

፱ በዚህም ፡ ዓለም ፡ ፍቅር ፡ አንድነት ፡ የኀጢአትም ፡ መሠረይ ፡ አይሆንላቸውም ።

፲ በልጆቻቸው ፡ ደስ ፡ አይላቸውምና ፡ የሚወዷቸው ፡ የልጆቻቸውን ፡ ሞት ፡ ያያሉ ፡ በልጆቻቸውም ፡ ጥፋት ፡ ጩኸው ፡ ያለቅሳሉ ።

፲፩ ለዘላለም ፡ ይለምናሉ ፡ ይቅርታም ፡ ፍቅርም ፡ አንድነትም ፡ አይደረግላቸው ።

፲፪ እኔ ፡ ሄኖክም ፡ ሂጂ ፡ አዛዝኤልን ፡ ፍቅር ፡ አንድነት ፡ አይደረግልህም ።

፲፫ ሊያጠፉህ ፡ ዕኑዕ ፡ መቻያ ፡ በንተ ፡ ታዘዘብህ ።

፲፬ ግፍን ፡ ስላስተማርህ ፡ የስድብንም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ስላስተማርህ ፡ ለሰው ፡ ልጆች ፡ የኀጢአትንና ፡ የግፍን ፡ ነገር ፡ ስላስተማርህ ፡ ዕረፍት ፡ ልመና ፡ ይቅርታ ፡ አይደረግልህም ፡ አልሁት ።

፲፭ ያን ፡ ጊዜ ፡ ሂጄ ፡ ለሁሉም ፡ አንድነት ፡ ነገርኋቸው ።

፲፮ እነሱም ፡ ሁሉ ፡ ፈሩ ፡ ፍራት ፡ መንቀጥቀጥም ፡ ያዛቸው ።

፲፯ ልጽፍላቸው ፡ ለነሱም ፡ የኀጢአታቸው ፡ መስተሥረያ ፡ ሊሆናቸው ፡ በሰማይ ፡ ወዳለ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፡ የልመናቸውን ፡ መታሰቢያ ፡ እኔ ፡ እንዳሳርግላቸው ፡ የልመናቸውን ፡ መታሰቢያ ፡ ጻፍልን ፡ ብለው ፡ ለመኑኝ ።

፲፰ እነሱ ፡ ከዛሬ ፡ ጀምረው ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጋራ ፡ መነጋገር ፡ አይችሉምና ፡ ከተፈረደባቸው ፡ በደል ፡ ኀፍረት ፡ የተነሣ ፡ ዓይናቸውን ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ቀና ፡ አድርገው ፡ ለማየት ፡ አይችሉምና ።

፲፱ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ስለ ፡ ሰውነታቸው ፡ የፍጹም ፡ ልመናቸውን ፡ መታሰቢያ ፡ ጻፍሁ ፡ የኀጢአታቸው ፡ መስተሥረያ ፡ የዘመንም ፡ ርዝመት ፡ ይሆንላቸው ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ለመኑኝ ፡ ያንዱንም ፡ ያንዱንም ፡ ሥራቸውን ፡ ጻፍኩ ።

፳ ሂጄም ፡ በውሆች ፡ ዳር ፡ ተቀመጥሁ ፡ ይቺውም ፡ በአርሞንኤም ፡ ግራ ፡ ቀኝ ፡ ያለች ፡ አገር ፡ ናት ።

፳፩ እስከንጎላች ፡ ድረስ ፡ የልመናቸውን ፡ መታሰቢያ ፡ ተናገርሁ ።

፳፪ እነሆ ፡ ሕልም ፡ መጣብኝ ፡ ራዕዮችም ፡ ተገለጡልኝ ።

፳፫ በሰማያዊ ፡ ማዕርግ ፡ ለነበሩ ፡ ለደቂቀ ፡ ሴት ፡ ነግሬ ፡ እሰድባቸው ፡ ዘንድ ፡ መቅሠፍት ፡ ያለበት ፡ ራዕይን ፡ አየሁ ።

፳፬ ነቅቼም ፡ ወደነሱ ፡ መጣሁ ፤ በሲኒሊርና ፡ በሊባኖስ ፡ መካከል ፡ ባለች ፡ በዑብልስያኢል ፡ ፊታቸውን ፡ ተከናንበው ፡ ሁሉም ፡ እያለቀሱ ፡ ተሰብስበው ፡ ተቀምጠው ፡ ነበር ።

፳፭ እኔም ፡ ተኝቼ ፡ ያየሁትን ፡ ራእይ ፡ ሁሉ ፡ በፊታቸው ፡ ተናገርኩ ።

፳፮ እውነት ፡ ነገር ፡ ያለበት ፡ ይህነን ፡ ቃል ፡ እናገር ፡ ዘንድ ፡ በደብር ፡ ቅዱስም ፡ ለነበሩ ፡ ለኀጢአታቸው ፡ ለሚተጉ ፡ ለደቂቀ ፡ ሴትም ፡ አስተምር ፡ ዘንድ ፡ ጀመርሁ ።

፳፯ የከበረ ፡ የገነነ ፡ ፈጣሪ ፡ በዚያች ፡ ራዕይ ፡ ንገራቸው ፡ ብሎ ፡ እንዳዘዘ ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡

የነበሩ ፡ ለኃጢአታቸው ፡ የሚተጉ ፡ የደቂቀ ፡ ሴት ፡ ዘለፋና ፡ እውነት ፡ ነገር ፡ የተጻፈበት ፡ መጽሐፍ ፡ ይህ ፡ ነው ።
፳፰፡ በሕሊና ፡ በሥጋዊ ፡ አንደበት ፡ እኔ ፡ ዛሬ ፡ የምናገረውን ፡ ነገር ፡ ተኝቼ ፡ አየሁ ፡ ይናገሩበት ፡ ዘንድ ፡ ለሰው ፡ አፍን ፡ የሰጠ ፡ የውቀትንም ፡ ነገር ፡ በልብ ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ፡ ፈጥሮ ፡ ለሰው ፡ ልቡናን ፡ ሰጠ ።
፳፱፡ ገናና ፡ እግዚአብሔር ፡ በደብር ፡ ቅዱስ ፡ ያሉ ፡ ደቂቀ ፡ ሴትን ፡ አስተምራቸው ፡ ዘንድ ፡ ለኔም ፡ ፈጥሮ ፡ ልቡናን ፡ ሰጥቶኛልና ፡ የምናገረውን ፡ ነገር ፡ ተኝቼ ፡ አየሁ ።
፴፡ እኔ ፡ ልመናችሁን ፡ ጻፍኩላችሁ ።
፴፩፡ በሕልሜ ፡ እንዲህ ፡ አሳየኝ ፡ ይህ ፡ ዓለም ፡ እንዲህ ፡ ፀንቶ ፡ በሚኖርበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ልመናችሁ ፡ አትደረግላችሁምና ።
፴፪፡ የመከራም ፡ መጨረሻም ፡ በናንተ ፡ ታዘዘችበችሁ ፡ የለመናችሁትም ፡ ልመና ፡ አይደረግላችሁም ።
፴፫፡ ከዛሬም ፡ ጀምራችሁ ፡ ይህ ፡ ዓለም ፡ ሁሉ ፡ እስኪያልፍ ፡ ድረስ ፡ ከፍ ፡ ወዳለ ፡ ማሰርጋችሁ ፡ አትወጡም ።
፴፬፡ ይህ ፡ ጸንቶ ፡ በሚኖርበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ሊያጠፉችሁ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ተናገረ ።
፴፭፡ ከዚህም ፡ አስቀድሞ ፡ የምትወዷቸው ፡ የልጆቻችሁን ፡ ጥፋት ፡ አያችሁ ።
፴፮፡ በፊታችሁ ፡ በሰይፍ ፡ ተቀራደው ፡ ያልቃሉ ፡ እንጂ ፡ ጥሪትንታቸው ፡ የላችሁም ።
፴፯፡ ስለናንተ ፡ የለመናችሁት ፡ ስለነሳቸውም ፡ የለመናችሁት ፡ ልመና ፡ አይደረግላችሁም ።
፴፰፡ ይህም ፡ ሁሉ ፡ የተደረገባችሁ ፡ እናንተ ፡ የብስጭት ፡ ኀዘን ፡ እያዘናችሁ ፡ ነው ፡ ከጻፍሁላችሁም ፡ መጽሐፍ ፡ ምንም ፡ ምንም ፡ እውነት ፡ ነገር ፡ አትናገሩም ።
፴፱፡ ለኔም ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ራዕይ ፡ ታየኝ ።
፵፡ እነሆ ፡ ደመናዎች ፡ በራዕይ ፡ ይጠሩኛል ፡ ጉምም ፡ ይጠራኛል ።
፵፩፡ መብረቆችና ፡ ከከቦችም ፡ በሩጫ ፡ ያስቸኩሉኛል ፡ ያስጨንቁኛል ።
፵፪፡ ነፋሶችም ፡ በሕልም ፡ ብር ፡ ብር ፡ ያደረጉኛል ፡ ያስቸኩሉኛል ፡ ( መላእክት ፡ ) ከምድር ፡ በላይ ፡ ወዳለ ፡ ሰማይም ፡ ይዘው ፡ አወጡኝ ።
፵፫፡ በበረድ ፡ ድንጊያ ፡ ወደ ፡ ተሠራች ፡ ማምብ ፡ እስትቀርብ ፡ ድረስ ፡ ወደ ፡ ቅጥሩ ፡ ገባሁ ።
፵፬፡ የእሳትም ፡ ቅጥር ፡ ይከበታል ፡ እኔንም ፡ ያስፈራኝ ፡ ጀመር ።
፵፭፡ ወደ ፡ እሳትም ፡ ቅጥር ፡ ገባቼ ፡ በበረድ ፡ ድንጊያ ፡ ወደ ፡ ተሠራ ፡ ታላቅ ፡ ቤት ፡ ቀረብሁ ።
፵፮፡ በበረድ ፡ ደንጊያዎች ፡ የተሠራ ፡ የዚያም ፡ ቤት ፡ ግድግዳ ፡ እንደ ፡ ሳንቃ ፡ ልዝብ ፡ ነው ።
፵፯፡ ምድሩም ፡ በረድ ፡ ነው ፡ ጠፈሩም ፡ እንደ ፡ መብረቅና ፡ እንደ ፡ ከከብ ፡ ነው ። (ቀለም ፡ ሰጋ ፡ )
፵፰፡ በቅጥሩና ፡ በቤቱም ፡ መካከል ፡ ከእሳት ፡ የተፈጠሩ ፡ ኪሩቤል ፡ አሉ ፡ ሰማያቸውም ፡ ውሀ ፡ ነው ።
በቅጽሩም ፡ ዙሪያ ፡ የሚነድ ፡ እሳት ፡ አለ ፡ ደጃፉም ፡ በእሳት ፡ ይቃጠላል ። ፵፱፡
ወደዚያም ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ ገባሁ ፡ እሳት ፡ እንደ ፡ መሆኑ ፡ ይሞቃል ፡ በረድ ፡ እንደ ፡ መሆኑ ፡ ይቀዘቅዛል ። ፶፡
ምንም ፡ ምንም ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ሕይወት ፡ በውስጡ ፡ የለም ፡ ፍራት ፡ ሸፈነኝ ፡ እንቅጥቅጥም ፡ ያዘኝ ፡ ታውኬ ፡ እየተንቀጠቀጥሁ ፡ በግምባሬ ፡ ወደቅሁ ፡ በሕልሜም ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ራዕይ ፡ አየሁ ። ፶፩፡
ከዚህ ፡ ቤትም ፡ የሚበልጥ ፡ ሌላ ፡ ቤት ፡ እነሆ ፡ አለ ። ፶፪፡
በፊቱም ፡ ደጃፉ ፡ ሁሉ ፡ የተከፈተ ፡ ነው ፡ በእሳት ፡ ቅጽርም ፡ የተሠራ ፡ ነው ። ፶፫፡
በሁሉም ፡ ይበልጣል ፡ በስብሐት ፡ በብርሃን ፡ በክብርም ፡ በወርድም ፡ በቁመትም ፡ የብርሃኑም ፡ ነገር ፡ የወርዱም ፡ የቁመቱም ፡ ነገር ፡ ለናንተ ፡ መናገር ፡ የማይቻለኝ ፡ እስኪሆን ፡ ድረስ ፡ በሁሉ ፡ ይበልጣል ። ፶፬፡
ወልወሉም ፡ እሳት ፡ ነው ፡ በላዩም ፡ መብረቅ ፡ የከከቦች ፡ መሮጫ ፡ አለበት ፡ ጠፈሩም ፡ የሚነድ ፡ እሳት ፡ ነው ። (እንደ ፡ ቀለም ፡ ሰጋ ፡ ) ፶፭፡
በውስጡም ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ዙፋን ፡ ፈጽሜ ፡ አየሁ ። ፶፮፡
መልኩም ፡ እንደ ፡ ውርጭ ፡ ነው ፡ አኀበሩም ፡ እንደሚያበራ ፡ ፀሐይ ፡ ነው ፡ የኪሩቤልም ፡ ቃል ፡ ይሰማል ። ፶፯፡
ከታላቁ ፡ ዙፋንም ፡ በታች ፡ የሚነድ ፡ የእሳት ፡ ፈሳሾች ፡ ይወጣሉ ፡ ፊቱንም ፡ ማየት ፡ አይቻላቸውም ። ፶፰፡
የክብር ፡ ባለቤት ፡ ጌታም ፡ በሱ ፡ ላይ ፡ ተቀምጧል ፡ መጐናጸፊያውም ፡ ከፀሐይ ፡ ይልቅ ፡ ያበራል ፡ ከበረድም ፡ ሁሉ ፡ ይነጣል ። ፶፱፡
ከመላእክትም ፡ ማንም ፡ ማን ፡ እሱ ፡ ወዳለበት ፡ መግባት ፡ አይችልም ፡ የከበረ ፡ የተመሰገነ ፡ ፊቱንም ፡ ማየት ፡ አይችልም ፡ ከሥጋዊ ፡ ከደማዊ ፡ ሰው ፡ ያንን ፡ እሳት ፡ ያይ ፡ ዘንድ ፡ ማየት ፡ የሚቻለው ፡ ማነው ። ፷፡
በዙሪያውም ፡ የሚነድ ፡ እሳት ፡ አለ ፡ በፊቱም ፡ ታላቅ ፡ እሳት ፡ ቆሟል ። (ደጀ ፡ ጠኒ ፡ መልአክ ፡ ነው ፡ ) ፷፩፡
በዙሪያው ፡ካሉ ፡ መላእክትም ፡ ወደሱ ፡ የሚቀርብ ፡ የለም ፡ የብዙ ፡ ብዙ ፡ መላእክትም ፡ በፊቱ ፡ አሉ ። ፷፪፡
እሱ ፡ ግን ፡ ከባሕርዩ ፡ የተለየች ፡ ምክርን ፡ አይወድም ። ፷፫፡
ወደሱ ፡ የሚቀርቡ ፡ መላእክትም ፡ በቀንም ፡ በሌሊትም ፡ ከሱ ፡ ፈጽመው ፡ አይርቁም ። ፷፬፡
እኔም ፡ እስከዚህ ፡ ድረስ ፡ እየተንቀጠቀጥሁ ፡ ፊቴን ፡ ተከናንቤ ፡ ነበርኩ ። ፷፭፡
ጌታም ፡ በንደበቱ ፡ ጠርቶ ፡ ሄኖክ ፡ ወደዚህ ፡ ቅረብ ፡ ለከበረ ፡ ቃሌም ፡ ታዘዝ ፡ አለኝ ። ፷፮፡
አንሥቶም ፡ እስከ ፡ ደጃፉ ፡ ድረስ ፡ አቀረበኝ ፡ ፷፯፡

እኔ ፡ ግን ፡ ፊቱን ፡ ደፍቼ ፡ ወደታች ፡ እመለከት ፡
ነበር ።
፳፰ ደግ ፡ ሰው ፡ የምትሆን ፡ ሕግንም ፡ በሰው ፡
ልቡና ፡ የምትጽፍ ፡ ሄኖክ ፡ በቃሉ ፡ ስማ ፡ አት
ፍራም ፡ አለኝ ።
፳፱ ወደዚህ ፡ ቅረብ ፡ ቃሌንም ፡ ስማ ፡ ለነሱ ፡ ልት
ለምንላቸው ፡ ለላኩህ ፡ ለኃጢአት ፡ ለሚተጉ ፡
ለደቂቀ ፡ ሴትም ፡ ሂደህ ፡ ንገራቸው ፡ አለኝ ።
፴ እናንተ ፡ ለሰው ፡ ልትለምኑ ፡ ይገባችሁ ፡ ነበር ፡
ሰው ፡ ግን ፡ ለናንተ ፡ ሊለምንላችሁ ፡ አይገባ
ውም ፡ ነበር ።
፴፩ ከፍ ፡ ያለ ፡ ደብር ፡ ቅዱስን ፡ ዘለዓለም ፡ ጸንቶ ፡
የሚኖር ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያትን ፡ ስለምን ፡
ተዋችሁት ፡ በላቸው ።
፴፪ ከሴቶችም ፡ ደረሳችሁ ፡ ከቃየልም ፡ ልጆች ፡
ጋራ ፡ ረከሳችሁ ።
፴፫ ለናንተ ፡ ሚስት ፡ አገባችሁ ፡ የቃየልም ፡ ልጆች ፡
እንደሚያደርጉት ፡ አደረጋችሁ ፡ ረጃጅም ፡ ልጆ
ችንም ፡ ወለዳችሁ ።
፴፬ ረቂቃን ፡ የምትሆኑ ፡ የከበራችሁ ፡ ዘለዓለም ፡
ጸንቶ ፡ በሚኖር ፡ ሕይወት ፡ ( መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ )
ደኅነኞች ፡ የምትሆኑ ፡ እናንተ ፡ ግን ፡ በሴቶች ፡
ረከሳችሁ ።
፴፭ በደማዊ ፡ በሥጋዊ ፡ ሥራም ፡ እንደ ፡ ወለዱ ፡
አደረጋችኋቸው ፡ እናንተም ፡ ሥጋዊ ፡ ደማዊ ፡
ሥራን ፡ ወደዳችሁ ፡ እነሱ ፡ ሥጋዊ ፡ ደማዊ ፡
ሥራን ፡ እንዲሠሩ ፡ እናንተም ፡ እንደነሱ ፡ ሠራ
ችሁ ።
፴፮ እነዚህም ፡ የሚሞቱ ፡ የሚጠፉ ፡ ናቸው ፡ የሚ
ሞቱ ፡ ስለሆነ ፡ ዘራቸውን ፡ በነሱ ፡ ይዘሩ ፡ ዘንድ ፡
ልጆችም ፡ ከነሱ ፡ ይወልዱ ፡ ዘንደ ' ሴቶችን ፡
ሰጠኋቸው ።
፴፯ በዚህ ፡ ዓለም ፡ እንደዚህ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡
ሥራ ፡ ሲሠራ ፡ ይኖራል ።
፴፰ እናንተ ፡ ግን ፡ ከዚህ ፡ አስቀድሞ ፡ ረቂቃንን ፡
ዘላለም ፡ ጸንቶ ፡ በሚኖር ፡ በልጅ ፡ ልጅ ፡ ዘመ
ንም ፡ በማያልፍ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ሕያ
ዋን ፡ ሁናችሁ ፡ ነበር ።
፴፱ የረቂቃን ፡ መላእክት ፡ ማደሪያቸው ፡ በሰማይ ፡
ነውና ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ሴቶችን ፡ ለናንተ ፡
ሚስቶች ፡ አላደረግኋቸውም ።
፵ አሁንም ፡ ወገኖቻቸው ፡ ከሚሆኑ ፡ ከደቂቀ ፡
ሴት ፡ የተወለዱ ፡ ረጃጅሞች ፡ ሰዎች ፡ በዚህ ፡
ዓለም ፡ ክፉ ፡ ልጆችን ፡ ይበላሉ ።
፵፩ ማዳሪያቸውም ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ይሆናል ።
፵፪ አባቶቻቸው ፡ ከደብር ፡ ቅዱስ ፡ ከወረዱ ፡ ከደ
ቂቀ ፡ ሴት ፡ ተወልደው ፡ ነበርና ፡ ወገኖቻቸው ፡
ከሚሆኑ ፡ ከደቂቀ ፡ ሴት ፡ ክፉ ፡ ልጆች ፡ ተወ
ለዱ ።
፵፫ ቀድሞ ፡ የንጽሕና ፡ መሠረት ፡ የነበሩ ፡ እነዚ
ህም ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ክፉ ፡ ልጆች ፡ ይሆናሉ ፡
ክፉ ፡ ልጆችም ፡ ይባላሉ ።
፵፬ በሰማይ ፡ የሚኖሩ ፡ ረቂቃን ፡ መላእክት ፡ ማደ
ሪያቸው ፡ በሰማይ ፡ ይሆናል ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡
የተወለዱ ፡ በምድር ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎችም ፡ ማደ
ሪያቸው ፡ በምድር ፡ ይሆናል ።
ከደመና ፡ የሚደርሱ ፡ ረጃጅሞች ፡ ሰዎችም ፡ ፵፭
ፈጽመው ፡ ይጠፋሉ ፡ እስበሳቸውም ፡ ይጣላሉ ፡
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሰውን ፡ ያጠፋሉ ።
በሰውም ፡ ኃዘንን ፡ ያደርጋሉ ፡ እነሳቸውም ፡ ፵፮
የሚበሉትን ፡ እህል ፡ ምንምን ፡ አያገኙም ።
ማየ ፡ አይህን ፡ ይጨልጣሉ ፡ እንጂ ፡ አይጠ ፵፯
ሙም ፡ በመኖርም ፡ አይታወቁም ።
ጥፋትና ፡ ሰልፍ ፡ በታዘዘበት ፡ ወራት ፡ ተወል ፵፰
ደዋልና ፡ እነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ኑረው ፡ በሴቶችና ፡
በወንዶች ፡ ላይ ፡ በጠላትነት ፡ አይነሱም ፡ አለ ።

ምዕራፍ ፡ ፭ ።

ወገኖቻቸው ፡ ከሚሆኑ ፡ ከደቂቀ ፡ ሴት ፡ ፩
የተወለዱ ፡ የረዓይት ፡ ሞታቸው ፡ በወጡበት ፡
በታ ፡ ነው ።
ሞታቸውም ፡ ሙሉን ፡ ሞት ፡ ይሁን ። ፪
ፍርድ ፡ ሳይደረግ ፡ የመከራ ፡ ፍጻሜ ፡ እስከሚ ፫
ደረግበት ፡ እስከ ፡ ዕለተ ፡ ምጽአት ፡ ድረስ ፡
እንደዚሁ ፡ ይጠፋሉ ፡ የከበረ ፡ መንግሥተ ፡
ሰማይ ፡ ከመሰጠቱ ፡ አስቀድሞ ፡ ሕግን ፡ በዘ
ነጉ ፡ ሰዎችና ፡ በደቂቀ ፡ ሴት ፡ ፍርድ ፡ ይጀመ
ራል ።
አሁንም ፡ ለነሱ ፡ ልትለምንላቸው ፡ የላኩሀን ፡ ፬
ከዚያ ፡ አስቀድሞ ፡ በደብር ፡ ቅዱስ ፡ የነበሩ ፡
ለኃጢአት ፡ የሚተጉ ፡ ደቂቀ ፡ ሴትን ፡ እንዲህ ፡
በላቸው ።
ዛሬም ፡ በደብር ፡ ቅዱስ ፡ ነበራችሁ ፡ የተሠወ ፭
ሩም ፡ ኃጢአቶች ፡ ገና ፡ አልተገለጡላችሁም ፡
ነበር ።
የተናቀ ፡ ምሥጢርንም ፡ አወቃችሁ ፡ በልቡ ፮
ናችሁም ፡ ዕናት ፡ ይህነን ፡ ነገር ፡ ለሴቶች ፡ ነገ
ራችሁ ።
ከዚህም ፡ ምሥጢር ፡ በወንዶችና ፡ በሴቶች ፡ ፯
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ክፋትን ፡ ያበዛሉ ፡ እንግዲህስ ፡
ፍቅር ፡ አንድነት ፡ የላችሁም ፡ በላቸው ፡ አለኝ ።
እንደ ፡ ቋያ ፡ የሚቃጠሉ ፡ ሰዎች ፡ ወዳሉበት ፡ ፰
ወደዚያ ፡ ወደ ፡ አንድ ፡ ቦታ ፡ መላእክት ፡ ወሰ
ዱኝ ፡ ሊታዩም ፡ በወደዱ ፡ ጊዜ ፡ ሰው ፡ ሆነው ፡
ይታያሉ ።
ጥቅል ፡ ነፋስ ፡ ወዳለበት ፡ ቦታ ፡ ራሱም ፡ እስከ ፡ ፱
ሰማይ ፡ ወደሚደርስ ፡ ተራራ ፡ ወሰዱኝ ። (ስነ ፡
ፍጥረት ፡ )
የሚያበሩ ፡ አራት ፡ ቦታዎችን ፡ አየሁ ፡ በጥል ፲
ቁም ፡ ዳርቻ ፡ ነጐድጓድ ፡ አለ ፡ የእሳት ፡ ቀስት ፡
የእሳት ፡ ፍላፃ ፡ ኰረኰሪያቸውም ፡ የእሳት ፡
ሰይፍ ፡ መብረቆችም ፡ ሁሉ ፡ አሉ ።
የሚናገር ፡ የመጣያ ፡ ወሀ ፡ እስከ ፡ አለበት ፡ ፲፩
ድረስ ፡ የምዕራብም ፡ እሳት ፡ እስካለበት ፡ ድረስ ፡
ወሰዱኝ ፡ ይኸውም ፡ የፀሐይን ፡ መግቢያ ፡
ሁሉ ፡ የሚይዝ ፡ ነው ።
እሳቱ ፡ እንደ ፡ ወሀ ፡ እስከሚፈስ ፡ እስከ ፡ እሳት ፡ ፲፪
ፈሳሽ ፡ ድረስ ፡ መጣሁ ፡ በምዕራብ ፡ ወዳለ ፡

ወደ ፡ ታላቁም ፡ ባሕር ፡ ያፈሳል ።
፲፫፤ ታላላቅ ፡ ወንዞችንም ፡ ሁሉ ፡ አየሁ ፡ እስከ ፡
ታላቁ ፡ (በርበሮስ ፡) ጨለማም ፡ ድረስ ፡ ደረ
ስኩ ፡ ሥጋዊ ፡ ደማዊ ፡ ሁሉም ፡ ወደሚመላለ
ስበት ፡ ሄድኩ ።
፲፬፤ የክረምት ፡ ጭጋጎች ፡ ያሉባቸው ፡ ተራሮች
ንም ፡ የወንዙንም ፡ ሁሉ ፡ ውሀ ፡ የሚፈስበትን ፡
አየሁ ፡ (ውቅያኖስንም ፡) ።
፲፭፤ በዚህ ፡ ዓለም ፡ የሚፈሱ ፡ የወንዞችንም ፡ ሁሉ ፡
አፋቸውን ፡ የውቅያኖስንም ፡ አፍ ፡ አየሁ ።
፲፮፤ የነፋሶችን ፡ ሁሉ ፡ በታዎችንም ፡ ሁሉ ፡ አየሁ ፡
ፍጥረቱን ፡ የምድሩንም ፡ ሁሉ ፡ መሠረቶች ፡
በነሳቸው ፡ እንዳስጌጠ ፡ አየሁ ፡ (አጸና) ።
፲፯፤ ባራቱ ፡ ማዕዘን ፡ ያለ ፡ አድማስንም ፡ አየሁ ፡
ምድርን ፡ ያጸኗት ፡ የጸናች ፡ ሰማይንም ፡ የሚ
ሸከሟት ፡ አራቱን ፡ ነፋሶች ፡ አየሁ ።
፲፰፤ የከበረች ፡ ሰማይንም ፡ ነፋሶች ፡ እንደ ፡ ዘረጓት ፡
አየሁ ።
፲፱፤ እነሳቸውም ፡ በምድርና ፡ በሰማይ ፡ መካከል ፡
ቁመው ፡ ይኖራሉ ፡ እነሳቸውም ፡ የሰማይ ፡
ምሰሶዎች ፡ ናቸው ።
፳፤ ሰማይን ፡ ዘርግተው ፡ የያዙ ፡ የፀሐይንም ፡
ክበብ ፡ የሚያገቡ ፡ ከዋክብትንም ፡ ሁሉ ፡ የሚ
ያገቡ ፡ ነፋሶችንም ፡ አየሁ ።
፳፩፤ ደመናዎችን ፡ የሚሸከሙ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ያሉ ፡
ነፋሶችንም ፡ አየሁ ።
፳፪፤ የመላእክትንም ፡ ቍጥር ፡ አየሁ ፡ በላይ ፡ ያለ ፡
ጠፈርን ፡ የሚያፀና ፡ በምድር ፡ ዳርቻ ፡ ያለ ፡
አድማሱን ፡ አየሁ ።
፳፫፤ ወደ ፡ አዜብም ፡ ሄድኩ ፡ በቀንም ፡ በሌሊትም ፡
ወደሚያበሩ ፡ ከከበረ ፡ ደንጊያ ፡ ወደሚበልጡ ፡
ወደ ፡ ሰባት ፡ ተራሮችም ፡ ሄድኩ ። (ዕንቍ ፡)
፳፬፤ ሦስቱ ፡ በምሥራቅ ፡ ሦስቱም ፡ በዓዜብ ፡ ናቸው ፡
በምሥራቅ ፡ ያለ ፡ ዕንቍ ፡ ግን ፡ አንዱ ፡ ቅጥ
ልጣል ፡ የሚባል ፡ ዕንቍ ፡ አንዱም ፡ ባሕር ፡
የሚባል ፡ ዕንቍ ፡ ነው ። አንዱ ፡ ደምርዕ ፡ የሚ
ባል ፡ ዕንቍ ፡ ነው ፡ በዓዜብ ፡ ያለ ፡ ቀይ ፡ ዕንቍ ፡
ነው ።
፳፭፤ መካከለኛው ፡ ግን ፡ ፒካ ፡ ከሚባል ፡ ዕንቍ ፡
እንደ ፡ ተሠራ ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መቀ
መጫ ፡ እስከ ፡ ሰማይ ፡ ይደርሳል ።
፳፮፤ የመቀመጫው ፡ አጎበሩ ፡ በሰንፒር ፡ ከሚባል ፡
ዕንቍ ፡ የተሠራ ፡ ነው ፡ በተራራው ፡ ሁሉ ፡ ያለ ፡
የሚቃጠል ፡ እሳትንም ፡ አየሁ ።
፳፯፤ በታላቅ ፡ ምድር ፡ መጨረሻ ፡ የሚሆን ፡ በታን ፡
በዚያ ፡ አየሁ ፡ ውሆዎች ፡ በዚያ ፡ ይሰበሰባሉ ።
፳፰፤ በሰማይ ፡ እሳት ፡ የሚቃጠሉ ፡ ደቂቀ ፡ ሴት ፡
የተጋዙበት ፡ ጥልቅ ፡ የሚሆን ፡ በዘ ሀ ፡ ዓለም ፡
ያለ ፡ ገሃነምንም ፡ አየሁ ።
፳፱፤ በእሳት ፡ የሚቃጠሉ ፡ ወደ ፡ ጥልቅም ፡ የሚወ
ርዱ ፡ ስፍር ፡ ቍጥር ፡ የሌላቸው ፡ የሰማይ ፡
ደቂቀ ፡ ሴትን ፡ በውስጣቸው ፡ አየሁ ፡ በዚያም ፡
በታ ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ርቀት ፡ ወደ ፡ ታችም ፡ ጥልቅ
ነት ፡ የለውም ።

በዚያም ፡ በገሃነም ፡ ላይ ፡ በታ ፡ አየሁ ፡ ለዚ ፴፤
ያም ፡ በታ ፡ በላይ ፡ ጠፈር ፡ በታችም ፡ መሠ
ረት ፡ የለውም ።
የምድረ ፡ በዳ ፡ በታ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በላዩ ፡ ፴፩፤
ውሀ ፡ የለም ፡ ወፎችም ፡ የሉም ።
በዚያም ፡ የሚያስፈራ ፡ በታን ፡ አየሁ ፡ እንደ ፴፪፤
ሚቃጠሉ ፡ እንደ ፡ ታላላቅ ፡ ተራሮች ፡ የሚቃ
ጠሉ ፡ ሰባት ፡ ከከቦችንም ፡ አየሁ ።
የሚጠይቀኝ ፡ ረቂቅ ፡ ባልደረባዬም ፡ እንደመ ፴፫፤
ሆኑ ፡ መልአኩ ፡ ይህ ፡ በታ ፡ የምድርና ፡ የሰ
ማይ ፡ መጨረሻ ፡ በታ ፡ ነው ።
ለሰማይ ፡ ከከቦች ፡ ለደቂቀ ፡ ሴት ፡ ለሰማይም ፡ ፴፬፤
ሠራዊት ፡ በእሳት ፡ ላይ ፡ ለሚገለባበጡ ፡ ከከበ
ችም ፡ ይህ ፡ የግዞት ፡ ቤት ፡ ሆናቸው ፡ አለኝ ።
በጊዜያቸው ፡ አልመጡምና ፡ በአእምሮ ፡ ፴፭፤
ፍጹም ፡ ከመሆናቸው ፡ አስቀድሞ ፡ የእግዚአ
ብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡ ያፈረሱ ፡ እኒህ ፡ ናቸው ።
የተሠወረ ፡ ፍዳቸውን ፡ በሚቀበሉበት ፡ ዘመን ፡ ፴፮፤
እስከ ፡ ኃጢአታቸው ፡ መጨረሻ ፡ ጊዜ ፡ ድረስ ፡
ተቈጥቶ ፡ አጋዛቸው ።
ሁርኤልም ፡ በዚህ ፡ በነገሩ ፡ ደቂቀ ፡ ሴት ፡ ከሴ ፴፯፤
ቶች ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ሆነው ፡ ሰውነቶቻቸው ፡
በፍዳ ፡ ተይዘው ፡ ይኖራሉ ።
በብዙ ፡ ወገንም ፡ አብነት ፡ ሁነዋቸው ፡ ሰዎችን ፡ ፴፰፤
አረከሷቸው ፡ ታላቅ ፡ በሆነ ፡ ጨርሰው ፡ እስኪ
ያጠፏቸው ፡ ድረስ ፡ በሚፈረድባቸው ፡ ገንዘብ ፡
ጽኑ ፡ ፍርድ ፡ በሚፈረድባት ፡ በዕለተ ፡ ምጽ
አት ፡ ይፈረድባቸዋልና ፡ ምዕመናን ፡ ለሥላሴ ፡
እንዲሠዉ ፡ እነሱም ፡ ለአጋንንት ፡ ይሠዉ ፡
ዘንድ ፡ ሰዎችን ፡ ያስቷቸዋል ።
ሚስቶቻቸውም ፡ ከፍ ፡ ባለ ፡ ማዕርግ ፡ የነበሩ ፡ ፴፱
የሴትን ፡ ልጆች ፡ አስተው ፡ ደጎና ፡ ሴቶችን ፡
ይሆናሉ ። (ይመስላሉ ፡ ሊ ፡ ነ ፡)
እኔ ፡ ሄኖክ ፡ በሁሉ ፡ ዳርቻ ፡ በአድማስ ፡ ሁኜ ፡ ፵፤
የኔን ፡ ብቻ ፡ ሥራ ፡ አየሁ ፡ ከሰዎችም ፡ እኔ ፡
እንዳየሁ ፡ ያየ ፡ የለም ።

## ምዕራፍ ፡ ፳ ።

ለምስጋና ፡ የሚተጉ ፡ የከበሩ ፡ የመላእክት ፡ ፩፤
ስማቸው ፡ ይህ ፡ ነው ።
ከከበሩ ፡ ከመላእክት ፡ አንዱ ፡ ሁርኤል ፡ በመ ፪፤
ብረቅ ፡ በነጐድጓድ ፡ የተሾመ ፡ ነው ።
በሰው ፡ ቍስል ፡ የተሾመ ፡ ከከበሩ ፡ ከመላእ ፫፤
ክት ፡ አንዱ ፡ ሩፋኤል ፡ ነው ።
ዲያብሎስን ፡ የሚበቀለው ፡ አጋንንትንም ፡ የሚ ፬፤
በቀላቸው ፡ ከከበሩ ፡ ከመላእክት ፡ አንዱ ፡ ራጉ
ኤል ፡ ነው ።
ለሰው ፡ በደረገው ፡ በጎነት ፡ ላይ ፡ ለሕዝቡ ፡ ፭፤
ታዛዥ ፡ ነውና ፡ ከከበሩ ፡ ከመላእክት ፡ አንዱ ፡
ሚካኤል ፡ ነው ።
አእምሯቸውን ፡ ባጡ ፡ ሰዎችም ፡ ላይ ፡ የተ ፮፤
ሾመ ፡ ከከበሩ ፡ ከመላእክት ፡ አንዱ ፡ ሠረቃ
ኤል ፡ ነው ።
በባቦች ፡ ላይ ፡ በገነትም ፡ ባሉ ፡ ጻድቃን ፡ ላይ ፡ ፯፤

በኪሩቤልም ፡ ላይ ፡ የተሾመ ፡ ከክቡሩ ፡ ከመላ
እክት ፡ አንዱ ፡ ገብርኤል ፡ ነው ።
፰፡ የሚሠራበት ፡ ሥራ ፡ እስከሌለበት ፡ ቦታ ፡ ድረስ ፡
ዞርኩ ፡ በዚያም ፡ የሚያስፈራ ፡ ሥራን ፡ አየሁ ።
የተዘጋጀ ፡ የሚያስፈራ ፡ የምድረ ፡ በዳ ፡ ቦታ ፡
ነው ፡ እንጂ ፡ በላይ ፡ ጠፈር ፡ በታችም ፡ መሠ
ረት ፡ የለውም ።
፱፡ በዚያም ፡ ቦታ ፡ እንደ ፡ ተላላቅ ፡ ተራሮች ፡ እንደ ፡
ቋያም ፡ ሲቃጠሉ ፡ አንድ ፡ ሆነው ፡ በሱ ፡ የተ
ጋዙ ፡ ሰባት ፡ የሰማይ ፡ ከከቦች ፡ አየሁ ። (ደቂቀ ፡
ሴት ፡ ናቸው ፡)
፲፡ ያን ፡ ጊዜም ፡ በምን ፡ ኃጢአታቸው ፡ ታስረው ፡
ተግዘዋል ፡ በምንስ ፡ ኃጢአታቸው ፡ በዚህ ፡
ወድቀዋል ፡ አልሁ ።
፲፩፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ያለ ፡ ወደ ፡ ወደደውም ፡ ሥራ ፡ የሚ
መራኝ ፡ ከክቡሩ ፡ ከመላእክት ፡ አንዱ ፡ ዑር
ኤልም ፡ ሄኖክ ፡ ስለምን ፡ ትጠይቃለህ ፡ የማን
ነስ ፡ ነገር ፡ ልትረዳ ፡ ትፈልጋለህ ፡ አለኝ ፡ አለ ።
፲፪፡ እኒህ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ትእዛዝ ፡
ያፈረሱ ፡ የሴት ፡ ልጆች ፡ ናቸው ፡ የዚህ ፡ ዓለም ፡
ዘመን ፡ ቍጥር ፡ ኃጢአታቸውም ፡ የሚሠራ
በት ፡ ወራት ፡ ቍጥር ፡ እስቲጨረስ ፡ ድረስ ፡
በዚህ ፡ ተግዘዋል ፡ አለኝ ።
፲፫፡ ከዚያም ፡ ከዚህ ፡ ቦታ ፡ ወደሚያስፈራ ፡ ወደ ፡
ሌላ ፡ ቦታ ፡ ሄድኩ ።
፲፬፡ በዚያም ፡ ቦታ ፡ የሚያስፈራ ፡ ሥራን ፡ አየሁ ፡
በዚያም ፡ ቦታ ፡ ፈጽሞ ፡ የሚቃጠል ፡ ታላቅ ፡
ቋያ ፡ አለ ፡ መጋዛም ፡ አለበት ፡ ድምበሩም ፡
በመምላት ፡ ፍጹም ፡ እስከ ፡ ሆነ ፡ እስከ ፡ ውቅያ
ኖስ ፡ ደርሷል ።
፲፭፡ ወደዚያው ፡ የሚያወርዷቸው ፡ ታላላቅ ፡ የእ
ሳት ፡ ምሰሶዎችም ፡ አሉ ፡ ( ደቂቀ ፡ ሴት ፡ ና ፡)
ቁመቱን ፡ ወርዱን ፡ ማየት ፡ አልቻልሁም ፡ መል
ኩንም ፡ ማየት ፡ ተሳነኝ ።
፲፮፡ ያን ፡ ጊዜም ፡ ይህ ፡ ቦታ ፡ እንዴት ፡ የሚያስ
ፈራ ፡ ነው ፡ ሊያውትም ፡ ደዌ ፡ ነው ፡ አልኩ ።
፲፯፡ ያን ፡ ጊዜም ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ያለ ፡ ከክቡሩ ፡ ከመላ
እክት ፡ አንዱ ፡ ዑርኤል ፡ መለሰልኝ ።
፲፰፡ ሄኖክ ፡ እንደዚህ ፡ አድርገህ ፡ መፍራትህ ፡ ምን
ድን ፡ ነው ፡ ስለዚህ ፡ ስለሚያስፈራ ፡ ቦታ ፡ መደ
ንገጥህ ፡ በዚህስ ፡ መከራ ፡ ገጸ ፡ መዓት ፡ መፍ
ራትህ ፡ ስለምንነው ፡ ብሎ ፡ መለሰልኝ ።
፲፱፡ ይህም ፡ ቦታ ፡ ለደቂቀ ፡ ሴት ፡ የግዞት ፡ ቤታ
ቸው ፡ ነው ፡ በዚያም ፡ ቦታ ፡ እስከ ፡ ዘለዓለም ፡
ድረስ ፡ ይጋዛሉ ።
፳፡ ከዚያም ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ቦታ ፡ ሄድሁ ፡ በምዕራ
ብም ፡ ረጅምና ፡ ታላቅ ፡ የሆነ ፡ ተራራን ፡ የጸና ፡
አለትንም ፡ አሳየኝ ። (አሕዛብን ፡)
፳፩፡ በጠገቡም ፡ ያማሩ ፡ አራት ፡ ቦታዎች ፡ አሉ ፡
በውስጡም ፡ ጥልቅነት ፡ ሰፊነት ፡ አለት ፡ እንደ ፡
መሆኑ ፡ ፈጽሞ ፡ የሚያድጥ ፡ አለት ፡ ነው ፡ ሊያ
ዩትም ፡ ጥልቅ ፡ ነው ፡ ጨለማም ፡ ነው ።
፳፪፡ ያን ፡ ጊዜም ፡ ከክቡሩ ፡ መላእክት ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡
ያለ ፡ አንዱ ፡ ሩፋኤል ፡ መለሰልኝ ።

እኒህ ፡ መልከም ፡ መልከም ፡ ቦታዎች ፡ የሞቱ ፡ ፳፫፡
ሰዎች ፡ ነፍሶች ፡ በነሱ ፡ ሊሰበሰቡባቸው ፡ እነ
ዚህ ፡ ለነሱ ፡ ተፈጠሩላቸው ፡ መላእክትም ፡
የደጋግ ፡ ሰዎች ፡ ልጆች ፡ ነፍሶችን ፡ ሁሉ ፡
በዚያ ፡ ይሰበስባሉ ።
ፍጹም ፡ መቻያቸውን ፡ እስተሚቀበሉበት ፡ ቀን ፡ ፳፬፡
ድረስ ፡ እስከ ፡ ጊዜያቸውም ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ እነ
ሱን ፡ የሚያኖሩባቸው ፡ እነዚህን ፡ ቦታዎች ፡
ሥላሴ ፡ ፈጠሩ ።
ይኸውም ፡ በነሱ ፡ ታላቅ ፡ መከራ ፡ እስኪደረግ ፡ ፳፭፡
ባቸው ፡ ድረስ ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ ነው ።
የደጋግ ፡ ሰዎች ፡ ልጆች ፡ ነፍሶችንም ፡ አየሁ ፡ ፳፮፡
እነሱ ፡ ሙተው ፡ ሳሉ ፡ ቃላቸው ፡ እስከ ፡ ሰማይ ፡
ይደርሳል ፡ ወንድሞቻቸውንም ፡ ይከሳሉ ፡ ይጣ
ላሉ ።
ያን ፡ ጊዜም ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ያለ ፡ ሩፋኤል ፡ ቃሉ ፡ ፳፯፡
እስከ ፡ ሰማይ ፡ ድረስ ፡ የሚደርስ ፡ የሚከስ ፡
ይኸ ፡ ነፍስ ፡ የማነው ፡ ነፍስ ፡ ብዬ ፡ ጠየቅሁት ።
ይህ ፡ ነፍስ ፡ ወንድሙ ፡ ቃየል ፡ በግፍ ፡ ከገደ ፡ ፳፰፡
ለው ፡ ከአቤል ፡ የተለየ ፡ ነፍስ ፡ ነው ፡ ልጁ ፡
ከዚህ ፡ ዓለም ፡ እስኪጠፋ ፡ ድረስ ፡ የልጅ ፡
ልጁም ፡ ከሰው ፡ ልጅ ፡ ተለይቶ ፡ እስኪጠፋ ፡
ቃየልን ፡ ይከሳል ፡ ብሎ ፡ መለሰልኝ ።
ያን ፡ ጊዜም ፡ የጻድቃንን ፡ ነገር ፡ የኃጥአንንም ፡ ፳፱፡
ነገር ፡ ሁሉ ፡ ጠየቅሁ ፡ አንዱ ፡ ካንዱ ፡ ስለምን ፡
ተለየ ፡ አልኩ ።
የሞቱ ፡ ሰዎችን ፡ ነፍስ ፡ ይለዩ ፡ ዘንድ ፡ እነዚህ ፡ ፴፡
ሦስት ፡ ቦታዎች ፡ ተፈጠሩ ፡ የጻድቃንም ፡ ነፍስ ፡
እንደዚህ ፡ ተለየ ፡ ብሎ ፡ መለሰልኝ ፡ ይህ ፡ ቦታ ፡
ብርሃን ፡ ያለበት ፡ የውሀ ፡ ምንጭ ፡ ነው ።
አሁን ፡ እንደ ፡ ተገናርሁት ፡ ለጻድቃን ፡ ቦታ ፡ ፴፩፡
እንደ ፡ ተፈጠረ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሞተው ፡ በተቀ
በሩ ፡ ጊዜ ፡ ሊኖሩበት ፡ ለኃጥአን ፡ ቦታ ፡ እንደ ፡
ተፈጠረላቸው ።
በሕይወተ ፡ ሥጋ ፡ ሳሉ ፡ በነሱ ፡ መከራ ፡ አል ፡ ፴፪፡
ተደረገባቸውም ።
መቻያ ፡ እስከሚቀበሉበት ፡ እስከ ፡ ዕለተ ፡ ምጽ ፡ ፴፫፡
ዓት ፡ ድረስ ፡ በዚች ፡ ታላቅ ፡ ጭንቅ ፡ ተይዘው ፡
ሊኖሩ ፡ በዚያ ፡ ቦታ ፡ ነፍሶቻቸው ፡ ከጻድቃን ፡
ነፍሳት ፡ ይለያሉ ፡ ለሚሳደቡም ፡ ሰዎች ፡ እስከ ፡
ዘላለሙ ፡ ድረስ ፡ መከራና ፡ መቅሠፍት ፡ ይደረ
ጉባቸዋል ፡ በሰውነታቸውም ፡ በቀል ፡ ትደረግ
ባቸዋለች ።
በዚያ ፡ ቦታ ፡ እስከ ፡ ዘላለሙ ፡ ዓሥሮ ፡ ያግዛቸ ፡ ፴፬፡
ዋል ፡ ምንም ፡ ከዕለተ ፡ ምጽዓት ፡ አስቀድሞ ፡
ቢሆን ፡ በዚያ ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ድረስ ፡ ዓሥሮ ፡
ያግዛቸዋል ።
የኃጥአን ፡ ነፍስ ፡ ቦታ ፡ እንደ ፡ ተለየ ፡ ወንድ ፡ ፴፭፡
ሞቻቸውን ፡ ለሚከሰሱ ፡ በኃጥአንም ፡ ወራት ፡
በሞቱ ፡ ጊዜ ፡ የጥፋታቸውን ፡ ነገር ፡ ለእግዚአ
ብሔር ፡ ለሚያሳዩ ፡ ለጻድቃንም ፡ ነፍስ ፡ ቦታ ፡
ተለየ ።
ለጻድቃንም ፡ ነፍስ ፡ ቦታ ፡ እንደ ፡ ተፈጠረ ፡ ፴፮፡
በደልን ፡ የጨረሱ ፡ ኃጥአንን ፡ ሆኑ ፡ እንጂ ፡

ጻድቃንን ፡ ላልሆኑ ፡ ለክፉዎች ፡ ሰዎች ፡ ነፍ
ስም ፡ ቦታ ፡ ተፈጠረ ፡ ከበደለኞችም ፡ ጋራ ፡
እንደነሱ ፡ በደለኞች ፡ ይሆናሉ ።
፴፯ ፡ መከራ ፡ በሚቀበሉበት ፡ በዕለተ ፡ ምጽአትም ፡
ነፍሳቸው ፡ አትሞትም ፡ ከፍዳም ፡ አይድኑም ።
፴፰ ፡ ያን ፡ ጊዜም ፡ የክብር ፡ ባለቤት ፡ ጌታን ፡ አመሰ
ገንሁት ፡ እስከ ፡ ዘላለሙ ፡ ድረስ ፡ ሁሉን ፡ የሚ
ገዛ ፡ የቸርነትና ፡ የጌትነት ፡ ባለቤት ፡ ጌታዬም ፡
የተመሰገነ ፡ ነው ፡ አልሁ ።
፴፱ ፡ ከዚያም ፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ በም
ዕራብ ፡ ወዳለ ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ቦታ ፡ ሄድሁ ።
፵ ፡ ሳያርፍ ፡ እየሮጠ ፡ የሚነድን ፡ እሳትንም ፡ አየሁ ፡
(ፀሐይ ፡ ነው) እኔ ፡ እንዳየሁት ፡ ፈጽሞ ፡ ሲሮጥ ፡
ይኖራል ፡ እንጂ ፡ በሌትና ፡ በቀን ፡ ከሩጫው ፡
አይገታም ፡ (አያርፍም ፡ ሲል ፡ ነው ፡)
፵፩ ፡ ይህ ፡ ዕረፍት ፡ የሌለው ፡ ምንድነው ፡ ብዬ ፡
ጠየቅሁ ።
፵፪ ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ያለ ፡ ከከበሩ ፡ ከመላእ
ክት ፡ አንዱ ፡ ራጉኤል ፡ መለሰልኝ ፡ ወደ ፡ ምዕ
ራብ ፡ ሊሮጥ ፡ ሩጫውን ፡ ያየኸው ፡ ይህ ፡ የሚ
ነድ ፡ እሳት ፡ ነው ፡ ይኸውም ፡ በሰማይ ፡ የሚ
ያበራ ፡ ፀሐይ ፡ ነው ።

ምዕራፍ ፡ ፳ ።

፩ ፡ ከዚያም ፡ ቦታ ፡ በምድር ፡ ወዳለ ፡ ወደሌላ ፡
ቦታ ፡ ሄድሁ ፡ በሌትና ፡ በቀን ፡ የሚቃጠል ፡
ቋያ ፡ ያለበት ፡ ተራራንም ፡ አሳየኝ ።
፪ ፡ ወደሱም ፡ ደጅ ፡ የከበሩ ፡ ሰባት ፡ ተራሮችን ፡
አየሁ ።
፫ ፡ ያየሁትም ፡ ሁሉ ፡ አንዱ ፡ ካንዱ ፡ ልውጥ ፡
ነው ፡ ያማሩና ፡ የከበሩ ፡ ድንጋዮችንም ፡ አየሁ ፡
ሁሉም ፡ የከበረ ፡ ነው ።
፬ ፡ መልካቸው ፡ የበራ ፡ ነው ፡ ፊታቸውም ፡ ያማረ ፡
ነው ፡ ሦስቱ ፡ በምሥራቅ ፡ ናቸው ፡ አንዱ ፡
ባንዱ ፡ ላይ ፡ የጸኑ ፡ ናቸው ።
፭ ፡ ሦስቱም ፡ በሰሜን ፡ በኩል ፡ ናቸው ፡ አንዱ ፡
ባንዱ ፡ ላይ ፡ የጸኑ ፡ ናቸው ። ጥልቆች ፡ ቆላ
ዎች ፡ አሉ ፡ ጠማሞችም ፡ ናቸው ፡ አንዲቱ ፡
አንዲቱን ፡ አትቀርበትም ።
፮ ፡ ሰባተኛውም ፡ ተራራ ፡ በነዚህ ፡ መካከል ፡ ነው ፡
ቁመታቸው ፡ እንደ ፡ አፍርንጊ ፡ ወምበር ፡
ሁሉም ፡ ይመሳሰላሉ ።
፯ ፡ መዓዛ ፡ ያላቸውም ፡ እንጨቶች ፡ ይከቡታል ፡
በመካከላቸውም ፡ አንድ ፡ እንጨት ፡ አለ ፡ በሸ
ተተኝም ፡ ጊዜ ፡ ከነሳቸው ፡ አንዱ ፡ ስንኳ ፡
እንደነሱ ፡ የሸተተኝ ፡ የለም ።
፰ ፡ ሌሎችም ፡ እንጨቶች ፡ ከሽቱው ፡ ሁሉ ፡ የሚ
ሸት ፡ እንደሱ ፡ የሚሸት ፡ አልሆነም ።
፱ ፡ ቅጠሉ ፡ አበባው ፡ እንጨቱም ፡ ለዘላለም ፡ አይ
ጠወልግም ።
፲ ፡ ፍሬውም ፡ ብዙ ፡ ነው ፡ እንደዘምባባም ፡ ፍሬ ፡
ንብብር ፡ ነው ።
፲፩ ፡ ያን ፡ ጊዜም ፡ ይህ ፡ እንጨት ፡ እነሆ ፡ ያማረ ፡
ነው ፡ ሊያውትም ፡ ፈጽሞ ፡ የተወደደ ፡ ነው ፡
ቅጠሉ ፡ ጽፍቅ ፡ ነው ፡ ፍሬው ፡ ንብብር ፡ ሊያ
ውትም ፡ ፈጽሞ ፡ የተወደደ ፡ ነው ፡ አልሁ ።
የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ያለ ፡ በላያቸው ፡ ፲፪ ፡
የተሾመ ፡ ፈጽመው ፡ ከከበሩ ፡ ከመላእክት ፡
አንዱ ፡ ሚካኤል ፡ መለሰልኝ ።
ሄኖክ ፡ የዚህን ፡ እንጨት ፡ ሽታ ፡ ነገር ፡ ምን ፡ ፲፫ ፡
ትጠይቃለህ ፡ ልታውቅስ ፡ ምን ፡ ትመረምራ
ለህ ፡ አለኝ ።
ያን ፡ ጊዜም ፡ እኔ ፡ ሄኖክ ፡ እንዲህ ፡ ብዬ ፡ መለ ፲፬ ፡
ስሁለት ፡ የእንጨቶችን ፡ ሁሉ ፡ ነገር ፡ ላውቅ ፡
እወዳለሁ ፡ ይልቁንም ፡ የዚህን ፡ እንጨት ፡
ነገር ፡ ላውቅ ፡ እወዳለሁ ፡ አልሁት ።
እሱም ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ መለሰልኝ ፡ ረጅም ፡ ፲፭ ፡
ሆኖ ፡ የምታየው ፡ ራሱ ፡ የጌታን ፡ መቀመጫ ፡
መስሎ ፡ ያየኸው ፡ ይህ ፡ ተራራ ፡ የተመሰገነ ፡
የገነነ ፡ የዘለዓለም ፡ ንጉሥ ፡ የሚሆን ፡ የክብር ፡
ባለቤት ፡ ይህችን ፡ ዓለም ፡ በበጎ ፡ ሊጎበኛት ፡
በወረደ ፡ ጊዜ ፡ የሚቀመጥበት ፡ ዙፋኑ ፡ ደብረ ፡
ሲና ፡ ነው ።
ይህም ፡ መዓዛ ፡ ያለው ፡ የተወደደ ፡ እንጨት ፡ ፲፮ ፡
ጌታ ፡ ሁሉን ፡ በተቀበለ ፡ ጊዜ ፡ እስከ ፡ ዘለዓ
ለም ፡ የሚሆን ፡ መከራም ፡ በተፈጸመ ፡ ጊዜ ፡
ጾኑ ፡ መከራ ፡ እስከሚደረግበት ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡
ከሥጋዊ ፡ ከደማዊ ፡ አንዱስ ፡ ስንኳ ፡ ሊነካው ፡
ሥልጣን ፡ የለውም ።
ለደጋጎች ፡ ለተዋረዱም ፡ ሰዎች ፡ ከዚህ ፡ እን ፲፯ ፡
ጨት ፡ ፍሬ ፡ ይሰጣቸዋል ፡ ለተመረጡም ፡ ሰዎች ፡
ደኅንነት ፡ ይሰጣል ።
የዘለዓለም ፡ ንጉሥ ፡ ወደሚሆን ፡ በደጊቱ ፡ ፲፰ ፡
ማደሪያ ፡ አንጻር ፡ በመስዕ ፡ በኩል ፡ በከበረ ፡
ቦታ ፡ ይተከላል ።
ያን ፡ ጊዜም ፡ ፈጽመው ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ። ፲፱ ፡
በየወገናቸው ፡ ወደ ፡ ከበረ ፡ ቦታ ፡ ሽቱን ፡ ያቀ ፳ ፡
ርቡለታል ፡ አባቶችህ ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ እንደኖሩ ፡
እነሱም ፡ በዚህም ፡ ዓለም ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ ይኖ
ራሉ ።
በዘመናቸውም ፡ መከራና ፡ አዘን ፡ መቅሠፍ ፳፩ ፡
ትና ፡ ድካምም ፡ አይዳስሳቸውም ፡ (አያገኛቸ
ውም) ።
እንደዚህ ፡ አድርጎ ፡ ወዳጆቹ ፡ ለሆኑት ፡ ሰዎች ፡ ፳፪ ፡
አዘጋጅቷልና ፡ እንደዚህም ፡ አድርጎ ፡ ፈጥሮ ፡
ይሰጧቸው ፡ ብሏልና ፡ የዘላለም ፡ ንጉሥ ፡ የሚ
ሆን ፡ የክብር ፡ ባለቤት ፡ ጌታን ፡ አመሰገንሁት ፡
አለ ።
ከዚያ ፡ ተነሥቼ ፡ ወደ ፡ ምድር ፡ መካከል ፡ ፳፫ ፡
ሄድሁ ፡ የከበረ ፡ የለመለመም ፡ እንጨት ፡ የተ
ቈረጠ ፡ ለምለሞ ፡ የሚኖር ፡ ጫፍ ፡ ያለበት ፡
ቦታንም ፡ አየሁ ። (ከነቢያት ፡ የተወለዱ ፡ ሐዋ
ርያት ፡ ናቸው ። )
በዚያም ፡ ቦታ ፡ የከበረ ፡ ተራራን ፡ አየሁ ፡ በተ ፳፬ ፡
ራራውም ፡ በታች ፡ በምሥራቁ ፡ አንጻር ፡ ውሀ ፡
አለ ፡ የሚፈሰውም ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ ነው ። (ትእ
ምርት ፡ ነው ። )
በምሥራቅም ፡ በኩል ፡ ከዚህ ፡ የሚበልጥ ፡ ፳፭ ፡

ሌላ ፡ ተራራንም ፡ አየሁ ።
፳፮፡ በመካከላቸውም ፡ ጥልቅ ፡ ቈላ ፡ አለ ። (አሕዛብ ፡ ናቸው ፡) ስፋት ፡ የለውም ፡ (ስፋሕ ፡ አእምሮ ፡ የላቸውም ፡) ውሀውም ፡ ለሷ ፡ እንደ ፡ ፈሰሰ ፡ ወደ ፡ ተራራው ፡ ይፈሳል ። (ትእምርቱ ፡ ለእስራኤል ፡ እንደ ፡ ተነገረ ፡ ለአሕዛብም ፡ ይነገራል ።)
፳፯፡ በዚህም ፡ በሁለተኛው ፡ ተራራ ፡ ምዕራብ ፡ አጠገብ ፡ ከሱ ፡ የሚያንስ ፡ ተራራ ፡ አለ ። (አርሞንዔም ፡ ነው ፡) ርዝመት ፡ የለውም ፡ በመካከላቸውም ፡ በበታቹ ፡ ቆላ ፡ አለ ።
፳፰፡ በሦስቱ ፡ ተራሮች ፡ ዳርቻ ፡ አጠገብ ፡ ጥልቅ ፡ የሆኑ ፡ የደረቁ ፡ ሌሎች ፡ ቈላዎች ፡ አሉ ።
፳፱፡ ቈላዎቹ ፡ ሁሉ ፡ ጥልቆች ፡ ናቸው ፡ ስፋት ፡ የለውም ፡ ከጽኑ ፡ ደንጊያ ፡ የተገኘ ፡ ጽኑ ፡ አለት ፡ ደንጊያ ፡ አለ ። (ከአሕዛብ ፡ የተወለዱ ፡ አሕዛብ ፡)
፴፡ በነሱ ፡ ላይ ፡ እንጨት ፡ ይተከላል ፡ (ሕግ ፡ ነው ፡) የአሕዛብን ፡ ነገር ፡ አደነቅሁ ፡ የሌላውንም ፡ ነገር ፡ አደነቅሁ ፡ (እስራኤል ፡) ይልቁንም ፡ የአሕዛብን ፡ ነገር ፡ አደነቅሁ ።
፴፩፡ ያን ፡ ጊዜም ፡ ይች ፡ የተባረከች ፡ ሁለመናዋ ፡ እንጨቶችን ፡ የተመላች ፡ ይቺ ፡ ምድር ፡ ለምን ፡ ተፈጠረች ። (መንግሥት ፡)
፴፪፡ ይችስ ፡ የተረገመች ፡ ቈላ ፡ በመካከላቸው ፡ ለምን ፡ ተፈጠረች ።
፴፫፡ ያን ፡ ጊዜም ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ያለ ፡ ከከበሩ ፡ ከመላእክት ፡ አንዱ ፡ ኡራኤል ፡ መለሰልኝ ፡ ይች ፡ የተረገመች ፡ ቈላ ፡ እስከ ፡ ዘላለሙ ፡ ሊኖሩበት ፡ ለተረገሙ ፡ ሰዎች ፡ ተፈጠረች ፡ አለኝ ።
፴፬፡ (ገሃነም ፡) በቃላቸው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ የማይገባ ፡ ነገርን ፡ የሚናገሩ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ በዚያ ፡ ቦታ ፡ ይሰበሰባሉ ።
፴፭፡ በጌትነቱ ፡ ጭንቅ ፡ ነገርን ፡ ስለ ፡ ተናገሩ ፡ በዚያ ፡ መላእክት ፡ ይሰበስቧቸዋል ፡ ቦታቸውም ፡ ይህ ፡ ነው ።
፴፮፡ በፍጻሜ ፡ ዘመን ፡ ለዘላለሙ ፡ በጻድቃን ፡ ፊት ፡ በውነት ፡ የሚቀበሉት ፡ የመከራቸው ፡ ምሳሌ ፡ በነሱ ፡ ይሆንባቸዋል ።
፴፯፡ ለሰው ፡ የሚያዝኑ ፡ የሚራሩ ፡ ጻድቃንም ፡ ለዘላለም ፡ የሚነግሥ ፡ የክብር ፡ ባለቤት ፡ ጌታን ፡ በዘመኑ ፡ ሁሉ ፡ በዚያ ፡ ቦታ ፡ አመሰገንሁት ።
፴፰፡ በተፈረደባቸውም ፡ ወራት ፡ እንዳደላቸው ፡ በቸርነቱ ፡ ያመሰግኑታል ።
፴፱፡ እኔም ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ የክብር ፡ ባለቤት ፡ ጌታን ፡ አመሰገንሁት ፡ ጌትነቱንም ፡ ተናገርሁለት ፡ ለገናናነቱም ፡ እንደሚገባ ፡ መጠን ፡ ስሙን ፡ ጠራሁ ።

ምዕራፍ ፡ ፰ ።

፩፡ ከዚያ ፡ በመድበራ ፡ ተራራ ፡ መካከል ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ሄድሁ ።
፪፡ ምድረ ፡ በዳውንም ፡ ብቻ ፡ አየሁ ። (እንደ ፡ አብረንታንት ፡)
ነገር ፡ ግን ፡ ከዚህ ፡ እንጨት ፡ ፍሬ ፡ የተገኙ ፡ ፫፡
እንጨቶችን ፡ ተመልቷል ።
ውሀም ፡ ከወደላይ ፡ ይመነጫል ፡ ሻሻቱውም ፡ ፬፡
በገዙቶ ፡ ይታያል ።
በመስዕ ፡ በኩል ፡ እንደ ፡ ፈሰሰ ፡ ወደ ፡ ምዕራብም ፡ ይፈሳል ፡ ከዚያም ፡ ወደ ፡ አራቱ ፡ ማዕዘን ፡ ይሄዳል ፡ ከዚያም ፡ ውሀና ፡ ጠል ፡ ይገኛል ። (ትእምርት ፡ ነው ፡) ፭፡
ከመድበራ ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ቦታ ፡ ሄጄ ፡ ወደዚህ ፡ ፮፡
ተራራ ፡ ምሥራቅ ፡ ቀረብሁ ።
በዚያም ፡ ሕግ ፡ የሚጠበቅባቸው ፡ እንጨቶ ፯፡
ችን ፡ አየሁ ፡ ይልቁንም ፡ የከርቤና ፡ የነጭ ፡ ዕጣን ፡ መዓዛ ፡ ያለባቸው ፡ የቅመም ፡ እንጨቶችን ፡ አየሁ ፡ እንጨቶችም ፡ አይመሳሰሉም ።
እነሱንም ፡ ካየሁ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ፰፡
ተራራ ፡ ሄድሁ ፡ ፈጽሚም ፡ የራቅሁ ፡ አይደለሁም ።
የማይገታ ፡ ውሀ ፡ ያለባቸው ፡ ሌላ ፡ የቈላዎች ፡ ፱፡
ቦታን ፡ አየሁ ።
ያማረ ፡ እንጨትንም ፡ አየሁ ፡ ሽታውም ፡ እንደ ፡ ፲፡
ለውዝ ፡ ሽታ ፡ ነው ።
በነዚህ ፡ ቈላዎች ፡ አጠገብም ፡ መዓዛ ፡ ያለው ፡ ፲፩፡
ሽታ ፡ አየሁ ።
እኒህን ፡ ካየሁ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ቀረ ፲፪፡
ብሁ ፡ በውስጡ ፡ እንጨቶች ፡ ያሉበት ፡ ሌላ ፡ ተራራንም ፡ አየሁ ።
ሣሬራ ፡ ከልበኔም ፡ እንደሚባል ፡ እንደ ፡ ነቂጥሮ ፡ ፲፫፡
ያለ ፡ ውሀ ፡ ይፈሳል ።
በዚያው ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ሆኜ ፡ ሌላ ፡ ተራራ ፡ ፲፬፡
አየሁ ፡ በውስጡም ፡ ዋግራ ፡ የሚባሉ ፡ እንጨቶች ፡ አሉበት ።
እኛም ፡ እንጨቶች ፡ ከርካዕ ፡ የሚባል ፡ ሽቱ ፡ ፲፭፡
የተመሉ ፡ ጽናትንም ፡ ያገኙ ፡ ናቸው ፡ ይህንንም ፡ ሽቱ ፡ በቈረጡት ፡ ጊዜ ፡ ከሽቱ ፡ ሁሉ ፡ ይበልጣል ።
እነዚህን ፡ ሽቶች ፡ ካየሁ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ መስዕ ፡ ፲፮፡
እየተመለከትሁ ፡ ወደ ፡ ተራሮች ፡ ሄድሁ ።
ያማረ ፡ ሽቱን ፡ መዓዛ ፡ ያላቸው ፡ እንጨቶች ፲፯፡
ንም ፡ ቀናንሞስ ፡ የሚባል ፡ ሽቱን ፡ ፕፕሬ ፡ የሚባል ፡ ሽቱን ፡ የተመሉ ፡ ሰባቱን ፡ ተራራዎች ፡ ሄድሁ ።
ከዚያም ፡ በነዚያ ፡ ተራሮች ፡ ላይ ፡ ርቄ ፡ ወደ ፡ ፲፰፡
ምሥራቅ ፡ ሄድሁ ።
ወደ ፡ ኤርትራ ፡ ባሕርም ፡ ሄድሁ ፡ ከዚያም ፡ ፲፱፡
ቦታ ፡ የራቅሁ ፡ ሆንሁ ።
ዙጡኤል ፡ በሚባል ፡ መልአክ ፡ (ዓቃቤ ፡ ገነት ፡ ፳፡
ነው ፡) በላይ ፡ አልፌ ፡ ሄድሁ ፡ በቸርነቱም ፡ ወደምትወረስ ፡ ገነት ፡ መጣሁ ።
ከኒህ ፡ እንጨቶች ፡ ወዲያ ፡ ብዙዎች ፡ ታላላ ፳፩፡
ቆች ፡ እንጨቶችን ፡ በዚያ ፡ በቅለው ፡ አየሁ ።
ሽታቸውም ፡ ያማረ ፡ ሲሆን ፡ ታላላቆች ፡ ናቸው ፡ ፳፪፡
ብርሃናቸውም ፡ ብዙ ፡ ነው ፡ እነሱም ፡ ያበራሉ ።
ከሱ ፡ በልተው ፡ ታላቅ ፡ ጥበብን ፡ የሚያውቁ ፳፫፡
በት ፡ የጥበብ ፡ እንጨትን ፡ አየሁ ፡ ተረርቃ

ሞም ፡ ይመስላል ።
፳፬ ፍሬውም ፡ እንደ ፡ ወይን ፡ ዘለላ ፡ እጅግ ፡ ያማረ ፡ ነው ፡ የዚያም ፡ እንጨት ፡ ሽታው ፡ ሄዶ ፡ ከሩቅ ፡ ይደርሳል ።
፳፭ ያማረ ፡ እንደ ፡ መሆኑ ፡ ሊያውትም ፡ ደስ ፡ እንደ ማሰኘቱ ፡ ይህ ፡ እንጨት ፡ ያማረ ፡ ነው ፡ አልሁ ።
፳፮ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ያለ ፡ የከበረ ፡ መልአኩ ፡ ሩፋኤ ልም ፡ መለሰልኝ ።
፳፯ ካንተ ፡ አስቀድመው ፡ የተፈጠሩ ፡ ባልቴት ፡ እናትህና ፡ ሽማግሌ ፡ አባትህ ፡ ( አዳምና ፡ ሔዋን ፡ ) ከሱ ፡ የበሉለት ፡ ጥበብን ፡ የሚገልጥ ፡ ዕፀ ፡ በለስ ፡ ይህ ፡ ነው ።
፳፰ ከሱም ፡ በልተው ፡ ክፉን ፡ ጥበብን ፡ አወቁት ፡ ዓይኖቻቸውም ፡ ተገለጡ ፡ ዕራቁታቸውንም ፡ እንዳለ ፡ አወቁ ፡ ከገነትም ፡ ተሰደዱ ፡ አለኝ ።
፳፱ ከዚያ ፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ ሄድሁ ፡ በዚያም ፡ ቦታ ፡ ታላላቅ ፡ አውሬዎችን ፡ አየሁ ።
፴ አንዱ ፡ ካንዱም ፡ ልውጥ ፡ ነው ፡ የወፎችም ፡ ፊታቸው ፡ ይለዋወጣል ፡ ጠጕራቸው ፡ ቃላቸ ውም ፡ አንዱ ፡ ካንዱ ፡ ይለዋወጣል ።
፴፩ በኒህ ፡ አውሬዎችም ፡ አጠገብ ፡ በምድር ፡ ዳርቻ ፡ ሰማይ ፡ በላዩ ፡ ያረፈበት ፡ አድማስን ፡ የተከፈቱ ፡ ደጃፎችንም ፡ አየሁ ።
፴፪ የሰማይ ፡ ከከቦችንም ፡ እንዲወጡ ፡ አየሁ ፡ ከዋ ክብት ፡ የሚወጡባቸው ፡ ደጃፎችንም ፡ ቈጠ ርሁ ።
፴፫ የየአንድ ፡ አንዳንዱን ፡ መውጫ ፡ ሁሉ ፡ በየቍ ጥራቸው ፡ ጻፍሁ ፡ ስማቸውን ፡ አናኗራቸውን ፡ ጊዜያቸውን ፡ ወራታቸውን ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ያለ ፡ መልአኩ ፡ ዑራኤል ፡ እንዳሳየኝ ፡ በንድነት ፡ ጻፍኩ ።
፴፬ ሁሉንም ፡ ለኔ ፡ አሳየኝ ፡ ጻፈው ፡ ዳግመኛ ፡ ስማቸውን ፡ ሥራታቸውንም ፡ ጻፈልኝ ።
፴፭ ከዚያ ፡ ተነሥቼ ፡ በምድር ፡ ዳርቻ ፡ ወደ ፡ መስዕ ፡ ሄድኩ ፡ በዚያም ፡ ሳለሁ ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡ ዳርቻ ፡ የሚያበራና ፡ ታላቅ ፡ ተአምራትን ፡ አየሁ ።
፴፮ ከዚያም ፡ ቦታ ፡ ሳለሁ ፡ የተከፈቱ ፡ የሰማይ ፡ ደጃፎችን ፡ አየሁ ፡ ሦስቱም ፡ ገጹ ፡ በሰማይ ፡ ናቸው ፡ ከነዚያም ፡ ነበያ ፡ አንዳንዱ ፡ ነፍሶች ፡ ይወጣሉ ።
፴፯ በመስዕ ፡ በኵል ፡ ነፋስ ፡ በነፈሰ ፡ ጊዜ ፡ ቀቅ ፡ በረዶ ፡ ውርጭም ፡ ዋግም ፡ ጤዛም ፡ ዝናምም ፡ ይፈሳል ፡ ከሦስቱ ፡ በንዲቱ ፡ መስኮት ፡ በበጎ ፡ ይነፍሳል ።
፴፰ በሁለቱ ፡ ሁሉ ፡ መስኮቶች ፡ ግን ፡ በነፈሱ ፡ ጊዜ ፡ በኃይል ፡ ይነፍሳሉ ፡ በዚህም ፡ ዓለም ፡ ጭንቅ ፡ መከራ ፡ ይሆናል ፡ እነሱም ፡ በኃይል ፡ ይነፍሳሉ ።
፴፱ ከዚያም ፡ ቦታ ፡ በምድር ፡ ዳርቻ ፡ ወደ ፡ ፀሐይ ፡ መግቢያ ፡ ሄድሁ ፡ በመስኮቶቹ ፡ ልክ ፡ በመው ጫውም ፡ ልክ ፡ በምሥራቅ ፡ እንዳየሁ ፡ በዚ ያም ፡ ቦታ ፡ የተከፈቱ ፡ ሦስት ፡ መስኮቶችን ፡ አየሁ ።

ከዚያም ፡ ቦታ ፡ በምድር ፡ ዳርቻ ፡ ወደ ፡ ዓዜብ ፡ ሄድሁ ። ፵
በዚያም ፡ ቦታ ፡ የተከፈቱ ፡ ሦስት ፡ የሰማይ ፡ መስኮቶችን ፡ አየሁ ፡ ከዚያም ፡ ቦታ ፡ ዋዕይ ፡ ጤዛ ፡ ዝናም ፡ ነፋስም ፡ ይነፍሳል ። ፵፩
ከዚያም ፡ ቦታ ፡ ተነሥቼ ፡ በሰማይ ፡ ዳርቻ ፡ ወደ ፡ ፀሐይ ፡ መውጫ ፡ ሄድሁ ። ፵፪
በዚያም ፡ ቦታ ፡ ሳለሁ ፡ በፀሐይ ፡ መውጫ ፡ በኵል ፡ የተከፈቱ ፡ ሦስት ፡ የሰማይ ፡ ደጃፎችን ፡ አየሁ ። ፵፫
በተናናሽ ፡ ደጃፎችም ፡ ላይ ፡ ከነዚሁ ፡ ደጃፎች ፡ በያንዳንዱ ፡ ተናናሾች ፡ የሰማይ ፡ ከከቦች ፡ ይገ ቡበታል ። ፵፬
በታየችላቸውም ፡ ጎዳና ፡ ወደ ፡ ፀሐይ ፡ መግ ቢያ ፡ ይሄዳሉ ። ፵፭
ይህንንም ፡ በየሁ ፡ ጊዜ ፡ ፈጣሪን ፡ አመሰገንሁ ፡ የፍጥረቱን ፡ ገናንነት ፡ ለሰዎች ፡ ሰውነቶችና ፡ ለመላእክት ፡ ሲገልጥ ፡ የሚያበሩና ፡ ታላላቅ ፡ ተአምራቶችን ፡ ያደረገ ፡ የክብር ፡ ባለቤት ፡ ጌታ ንም ፡ በየጊዜው ፡ አመሰግነዋለሁ ። ፵፮
ፍጥረቱን ፡ ያመሰግኑ ፡ ዘንድ ፡ ፍጥረቱም ፡ ሁሉ ፡ የኃይሉን ፡ ሥራ ፡ ያዩ ፡ ዘንድ ፡ ታላቅ ፡ የሆነ ፡ የቃሉንም ፡ ሥራ ፡ ያመሰግኑ ፡ ዘንድ ፡ እሱንም ፡ ለዘላለሙ ፡ ያመሰግኑት ፡ ዘንድ ፡ ይኸ ንን ፡ አደረገ ። ፵፯

ምዕራፍ ፡ ፱ ።

የያሬድ ፡ ልጅ ፡ ሄኖክ ፡ በሌላ ፡ ጊዜ ፡ ያየው ፡ ጥበብ ፡ ያለበት ፡ ራዕይ ፡ ይህ ፡ ነው ፡ ያሬድን ፡ የመላልኤል ፡ ልጅ ፡ አለው ፡ መላልኤልን ፡ የቃ ይናን ፡ ልጅ ፡ አለው ፡ ቃይናንን ፡ የሄኖስ ፡ ልጅ ፡ አለው ፡ ሄኖስን ፡ የሴት ፡ ልጅ ፡ አለው ፡ ሴትን ፡ የአዳም ፡ ልጅ ፡ አለው ። ፩
በዚህም ፡ ዓለም ፡ ላሉ ፡ ሰዎች ፡ እናገረው ፡ ዘንድ ፡ የጀመርሁት ፡ የዘጠኙ ፡ ሕጋጋት ፡ አበ ጋዝ ፡ ይህ ፡ ኢታምልክ ፡ ነው ። ፪
የቀድሞ ፡ ሰዎች ፡ ይኸንን ፡ ነገር ፡ ሰሙ ፡ በኋ ላም ፡ የተነሣችሁ ፡ ሰዎች ፡ በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ፊት ፡ የምናገረው ፡ የከበረ ፡ የኢታምልክን ፡ ነገር ፡ አስተውሉ ። ፫
የለዚህ ፡ የአበው ፡ ነገራቸው ፡ ከዘጠኙ ፡ ሕገ ጋት ፡ ኢታምልክ ፡ ይበልጣል ፡ ማለት ፡ ነው ፤ እኛም ፡ በኋላ ፡ የተነሣን ፡ ሰዎች ፡ ከዘጠኙ ፡ ሕገጋት ፡ ኢታምልክ ፡ ትበልጣለች ፡ ማለትን ፡ አንከለክልም ። ፬
እኔ ፡ እንዳሰብሁት ፡ ዘላለም ፡ ጸንቶ ፡ የሚኖር ፡ የሕይወት ፡ እድል ፡ ከሱ ፡ የተሰጠኝ ፡ የመላእ ክት ፡ ጌታ ፡ እንደ ፡ ወደደ ፡ ዛሬ ፡ የያዝሁት ፡ ጥበብ ፡ ከመላእክት ፡ ፊት ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ አልተሰጠኝም ፡ ነበር ። ፭
ሦስት ፡ ነገሮችም ፡ ተገለጡልኝ ። ፮
እኔም ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ለሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ እነግ ራቸው ፡ ጀመር ። ፯
መጀመሪያው ፡ ነገር ፡ ይህ ፡ ነው ፡ የደጋጎቹ ፡ ፰

# የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ሃይማኖትና ሥርዓት



እጅ ፡ ይወድቃሉ ።
፪ ፤ በመጨረሻዋም ፡ ከበጎ ፡ ሥራቸው ፡ የተነሣ ፡
ቤት ፡ ንብረት ፡ ያደርጋሉ ፡ እስከ ፡ ዘለዓለም ፡
ሊመሰገንበት ፡ ለገናና ፡ ንጉሥ ፡ ለእግዚአብ
ሔር ፡ ደብተራ ፡ ኦሪት ፡ ይሠራል ።
፫ ፤ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ በዘጠኘኛይቱ ፡ ሱባዔ ፡ ለሰው ፡
ሁሉ ፡ እውነተኛይቱ ፡ ሕግ ፡ ትገለጣለች ።
፬ ፤ ሕገ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የዘነጉ ፡ ሰዎችም ፡ ሥራ ፡
ሁሉ ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ይጠፋል ፡ ሰውም ፡ ለጥ
ፋት ፡ ይቈጠራል ፡ ይህንንም ፡ አይተው ፡ ሌሎች ፡
ሰዎች ፡ የቀናች ፡ ሥራን ፡ ይመለከታሉ ።
፭ ፤ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በሥረኛይቱ ፡ ሱባዔ ፡ ሰባት ፡
እጅ ፡ የሚሆን ፡ የዘላለም ፡ ፍርድ ፡ ይደረግበታል ።
፮ ፤ በደቂቀ ፡ ሴትም ፡ ፍርድ ፡ ትደረጋለች ፡ በመላ
እክት ፡ መካከል ፡ ጸንቶ ፡ የሚኖር ፡ ደገኛ ፡ መን
ግሥተ ፡ ሰማያትም ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ይሰጣል ፡
ይባላል ።
፯ ፤ የቀድሞ ፡ ሰማይ ፡ ፈጽሞ ፡ ያልፋል ፡ ይባላል ፡
አዲስ ፡ (ጠፈር ፡) መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ይሰ
ጣል ፡ ይባላል ፡ የሰማይ ፡ ሠራዊት ፡ ጻድቃንም ፡
ሁሉ ፡ ሰባት ፡ እጥፍ ፡ ብርሃንን ፡ ለዘላለሙ ፡
ያበራሉ ።
፰ ፤ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ስፍር ፡ ቍጥር ፡ የሌላቸው ፡
ብዙ ፡ ሱባዔዎች ፡ በቸርነቱና ፡ በይቅርታ ፡ ለዘ
ላለሙ ፡ ይደረጋሉ ፡ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ኃጢ
አት ፡ እስተዘላለሙ ፡ ትሠራለች ፡ አትሠራም ።
፱ ፤ አሁንም ፡ ልጆቼ ፡ እነግራችኋለሁ ፡ የግፍ ፡ ሥራ
ዎችንና ፡ የበጎ ፡ ሥራዎችን ፡ ገልጬ ፡ አስተም
ራችኋለሁ ።
፲ ፤ ዳግመኛ ፡ የሚመጣባችሁን ፡ መከራ ፡ ታውቁ ፡
ዘንድ ፡ ገልጬ ፡ አስተምራችኋለሁ ፡ አሁንም ፡
ልጆቼ ፡ ስሙኝ ፡ በበጎ ፡ ሥራዎች ፡ ጸንታችሁ ፡
ኑሩ ።
፲፩ ፤ በግፍ ፡ ሥራ ፡ ጸንተው ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡
ሁሉ ፡ ለዘላለሙ ፡ ይጠፋሉ ፡ ልጄ ፡ በግፍ ፡
ሥራዎች ፡ ጸንታችሁ ፡ አትኑሩ ፡ እላችኋለሁ ።
፲፪ ፤ ሕግን ፡ በሰው ፡ ልቡና ፡ ከምጽፍ ፡ ከሰው ፡ ሁሉ ፡
ክቡር ፡ የዓለሙም ፡ ሁሉ ፡ መምህር ፡ ከምሆን ፡
ከኔ ፡ ከሄኖክ ፡ የተጻፈ ።
፲፫ ፤ ይህ ፡ ሁሉ ፡ የጥበብ ፡ ትምህርት ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡
ለሚኖሩ ፡ ለልጆቼ ፡ ሁሉ ፡ ፍቅርንና ፡ የቀና ፡
ነገርን ፡ ለሚሠሩ ፡ ኋላ ፡ ለሚወለዱ ፡ ልጆችም ፡
ትድረስ ።
፲፬ ፤ ንጹሕ ፡ ክቡር ፡ ገናናም ፡ የሚሆን ፡ ጌታ ፡ ለሰው ፡
ሁሉ ፡ መዋዕለ ፡ ንስሐን ፡ ሰጥቷልና ፡ ሰውነታ
ችሁ ፡ በአዝማን ፡ መንግሥተ ፡ ሰማይን ፡ እንዳ
ታዝን ፡ ትሁን ።
፲፭ ፤ ጻድቅ ፡ ሰው ፡ ከንዋመ ፡ ሐኬት ፡ ይለያል ፡ ወደ ፡
እውነት ፡ ሥራዎችም ፡ ይሔዳል ።
፲፮ ፤ ሥራውም ፡ ሁሉ ፡ አኗኗሩም ፡ በይቅርታና ፡
በቸርነት ፡ ነው ፡ ደጉንም ፡ ሰው ፡ ለዘላለሙ ፡
ይቅር ፡ ይለዋል ፡ በሱም ፡ ለዘለዓለሙ ፡ የቀና ፡
ሥራን ፡ ይሰጠዋል ፡ ሥልጣንንም ፡ ይሰጠዋል ።
፲፯ ፤ ቸርነቱ ፡ በእውነትም ፡ ሥራ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፡
ዕውቀትም ፡ ለዘላለሙ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፡ በለ
ማወቅ ፡ የተሠራች ፡ ኃጢአትም ፡ እስተዘላ
ለሙ ፡ ትጠፋለች ፡ ከዚያችም ፡ ቀን ፡ ጀምሮ ፡
እስተዘላለሙ ፡ እንግዲህ ፡ ወዲያ ፡ ትወራለች ፡
አትባልም ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ሄኖክ ፡ እንዲህ ፡ ሆነ ፡ ከመጻሕ ፲፰ ፤
ፍት ፡ እየተጠቀሰ ፡ ይናገር ፡ ጀመረ ።
ሄኖክ ፡ የሕጋውያንን ፡ ነገር ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ፲፱ ፤
ያሉ ፡ የደናግልንም ፡ ነገር ፡ ሕግን ፡ የሚጠብቅ ፡
የቀና ፡ ሥራንም ፡ የሚሠራ ፡ የአብርሃምንም ፡
ነገር ፡ ተናገረ ፡ ልጆቼ ፡ እነዚህን ፡ ነገሮች ፡
ፈጽሜ ፡ እነግራችኋለሁ ፡ አለ ።
በሰማይ ፡ የታየኝን ፡ ራዕይ ፡ የከበሩ ፡ ከሆኑ ፡ ፳ ፤
ከመላእክት ፡ ቃል ፡ ሰምቼ ፡ ያወቅሁትን ፡ በሰ
ማይ ፡ ሰሌዳነትም ፡ አይቼ ፡ ልብ ፡ ያደረግሁትን ፡
እኔ ፡ ሄኖክ ፡ እነግራችኋለሁ ።
ሄኖክም ፡ ከመጻሕፍት ፡ እየጠቀሰ ፡ ይናገር ፡ ፳፩ ፤
ጀመረ ፡ በለአእምሮ ፡ የምሆን ፡ እኔ ፡ ሄኖክ ፡
በመጀመሪያይቱ ፡ ሱባዔ ፡ ተወለድሁ ።
እውነተኛ ፡ ፍርድ ፡ እስኪደረግ ፡ ድረስ ፡ ጌታ ፡ ፳፪ ፤
የሰውን ፡ ኃጢአት ፡ ታገሠ ፡ ከኔም ፡ በኋላ ፡
በሁለተኛይቱ ፡ ሰባዔ ፡ ጽኑ ፡ ኃጢአት ፡ ትሠ
ራለች ።
ተንኰልም ፡ ጸናች ፡ በሷም ፡ የመጀመሪያይቱ ፡ ፳፫ ፤
መከራ ፡ መጨረሻ ፡ ትደረጋለች ። ( ማየ ፡ አይኅ ፡
ነው ፡ )
ኖኅም ፡ በሷ ፡ ከማየ ፡ አይህ ፡ ይድናል ፡ ዘመ ፳፬ ፤
ኑም ፡ ከተጨረሰ ፡ በኋላ ፡ ግፍ ፡ ትሠራለች ፡
እሱንም ፡ ለበደሉ ፡ ሰዎች ፡ የልሳን ፡ መለያየ
ትን ፡ ያደርጋል ። ( በቋንቋ ፡ )
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በሦስተኛይቱ ፡ ሱባዔ ፡ በመ ፳፭ ፤
ጨረሻዋ ፡ እውነተኛ ፡ ሕግን ፡ ለመጠበቅ ፡ አብ
ርሃም ፡ ይመረጣል ፡ ከሱም ፡ ለዘላለሙ ፡ ሕግን ፡
የሚጠብቅ ፡ ይስሐቅ ፡ ይወለዳል ።
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ባራተኛይቱ ፡ ሱባዔ ፡ በመጨ ፳፮
ረሻዋ ፡ ነቢያትና ፡ ካህናት ፡ ራዕይ ፡ ያያሉ ፡
ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ዘመን ፡ ጸንታ ፡ የምትኖር ፡ ሕገ ፡
ኦሪትም ፡ ትሠራለች ፡ ደብተራ ፡ ኦሪትም ፡ ትሠ
ራላቸዋለች ።
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በምስተኛይቱ ፡ ሱባዔ ፡ በመ ፳፯ ፤
ጨረሻዋ ፡ መንግሥትና ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ እስ
ተዘላለሙ ፡ ሊኖር ፡ ይሠራል ።
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በስድስተኛይቱ ፡ ሱባዔ ፡ በሷ ፡ ፳፰ ፤
የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ደንቆሮዎች ፡ ናቸው ፡
የሁሉም ፡ ልቡናቸው ፡ ከጥበብ ፡ ይለያል ፡
በሷም ፡ ኤልያስ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ያርጋል ።
በመጨረሻዋም ፡ የመንግሥቱ ፡ ቤት ፡ በእሳት ፡ ፳፱ ፤
ይቃጠላል ፡ የተመረጡ ፡ የመንግሥትም ፡ ዘመ
ዶች ፡ ሁሉ ፡ በሷ ፡ ይበተናሉ ።
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በሰባተኛይቱ ፡ ሱባዔ ፡ ወንጀ ፴ ፤
ለኛ ፡ ኃጢአቷ ፡ ብዙ ፡ የሆነ ፡ ሥራዋም ፡ ሁሉ ፡
ወንጀል ፡ የሚሆን ፡ ልጅ ፡ ትነሣለች ።
በመጨረሻዋ ፡ ዘላለም ፡ ጸንቶ ፡ የሚኖር ፡ ሕግን ፡ ፴፩ ፤
ከጠበቀ ፡ ከአብርሃም ፡ የተወለዱ ፡ የትምርታ

ቸው ፡ ዋጋ ፡ ሰባት ፡ እጥፍ ፡ ሆኖ ፡ የሚሰጣ
ቸው ፡ ነቢያት ፡ ፍጥረቱን ፡ ሁሉ ፡ ለማስተማር ፡
ይመረጣሉ ።
፺፪፣ ከሰው ፡ ከተወለደ ፡ ሁሉ ፡ የከበረ ፡ የጌታ ፡
ቃሉን ፡ ሰምቶ ፡ የማይተዋወክ ፡ ማነው ፡ አሳቡ
ንስ ፡ ያስብ ፡ ዘንድ ፡ የሚችል ፡ ማነው ።
፺፫፣ ሰማይን ፡ ሥራዋንም ፡ ሁሉ ፡ ቀና ፡ ብሎ ፡
ማየት ፡ የሚችል ፡ ማነው ።
፺፬፣ የሰማይን ፡ ሥራ ፡ መርምሮ ፡ ማወቅ ፡ የሚቻ
ለው ፡ ከሥጋውም ፡ ለይቶ ፡ ነፍሱን ፡ ከነፍ
ሱም ፡ ለይቶ ፡ ሥጋውን ፡ ማየት ፡ የሚቻለው ፡
ይህ ፡ ነፍሴ ፡ ነው ፡ ይህ ፡ ሥጋዬ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡
መናገር ፡ የሚቻለው ፡ ማነው ፡ ይህም ፡ ባይ
ሆን ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ መውጣት ፡ የመላእክትን ፡
ክንፍ ፡ አይቶ ፡ የሚያስባቸው ፡ ይህም ፡ ባይ
ሆን ፡ እንደነሳቸው ፡ ማድረግ ፡ የሚቻለው ፡
ማነው ።
፺፭፣ የምድርን ፡ አቄልቋይዋን ፡ ወርዷን ፡ ምንም ፡
እንደ ፡ ሆነ ፡ ማወቅ ፡ የሚችል ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡
ማነው ።
፺፮፣ የነዚህ ፡ ሁሉ ፡ ልካቸው ፡ ለማን ፡ ተገለጠ ፡ የሰ
ማይን ፡ ምጥቀቷን ፡ ርዝመቷን ፡ ምንም ፡ እንደ ፡
ሆነ ፡ የፀናችበትም ፡ በምንም ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
መርምሮ ፡ ማወቅ ፡ የሚችል ፡ የከከቦችም ፡
ቍጥራቸው ፡ ምን ፡ ያህል ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ፀሐይ ፡
ጨረቃም ፡ ሁሉ ፡ በየትም ፡ እንዲያርፉ ፡ ማወቅ ፡
የሚቻለው ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ቢኖር ፡ በሱ ፡ ነው ።

ምዕራፍ ፡ ፺፬ ።

፩፣ አሁንም ፡ ልጆቼ ፡ እውነተኛይቱን ፡ ሕግ ፡
ውደዷት ፡ የውነት ፡ ሥራዎችን ፡ ይቀበሏቸው ፡
ዘንድ ፡ ይገባልና ፡ በሷም ፡ ጸንታችሁ ፡ ኑሩ ፡
እላችኋለሁ ።
፪፣ የግፍ ፡ ሥራዎች ፡ ግን ፡ ፈጥነው ፡ ይጠፋሉ ፡
ያንሳሉ ፡ በደግነት ፡ ለታወቁ ፡ ሰዎችም ፡ ከልጅ ፡
ልጅ ፡ ጀምሮ ፡ የሞትና ፡ የግፍ ፡ ሥራዎች ፡ ይገ
ለጣሉ ፡ ሰዎችም ፡ ከነሳቸው ፡ ይርቃሉ ፡ እነ
ሱንም ፡ አይከተሏቸውም ።
፫፣ አሁንም ፡ ለናንተ ፡ ለወዳጆቼ ፡ በግፍና ፡ በክፉ ፡
ሥራዎች ፡ ሞትን ፡ በሚያመጡ ፡ ሥራዎች ፡
ጸንታችሁ ፡ አትኑሩ ፡ እውነት ፡ ነገርን ፡ የተመ
ረጠች ፡ ድኅነታችሁንም ፡ ለናንተ ፡ ፈጽማችሁ ፡
ውደዱ ፡ እንዷ ፡ እንዳትጠፉ ፡ ወደነሱ ፡ አትቅ
ረቡ ፡ እላችኋለሁ ።
፬፣ በፍቅር ፡ ሥራዎችም ፡ ጸንታችሁ ፡ ኑሩ ፡ ትድ
ናላችሁ ፡ በተድላ ፡ ደስታውም ፡ ትዘጋጃላችሁ ፡
በልቡናችሁም ፡ አሳብ ፡ ሕጉን ፡ ትይዛላችሁ ።
፭፣ ክፉ ፡ ጥበብን ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ደጋጎች ፡ ሰዎ
ችን ፡ ክፉዎች ፡ ሰዎች ፡ እንዲፈትኗቸው ፡ አው
ቃለሁና ፡ ነገሬ ፡ ከልቡናችሁ ፡ አይጥፋ ፡ ለኃ
ጢአትም ፡ ልቡና ፡ ሁሉ ፡ አይገኝላት ፡ ሕግ ፡
ቢያፈርሱ ፡ የሚመጣው ፡ መከራ ፡ ሁሉ ፡ አያን
ስም ።
፮፣ እነሱ ፡ ፈጥነው ፡ ይጠፋሉና ፡ ፍቅር ፡ አንድነ
ትም ፡ የላቸውምና ፡ ሐሰት ፡ ነገርን ፡ ግፍንም ፡
ትንኰልንም ፡ አጥንተው ፡ ለሚሠሯት ፡ ሰዎች ፡
ወዮላቸው ።
ከሥር ፡ ከመሠረታቸው ፡ ሁሉ ፡ ይጠፋሉና ፡ ፯፣
በሰይፍም ፡ ተቀራደው ፡ ያልቃሉና ፡ ወርቅን ፡
ብርንም ፡ የሚሰበስቧት ፡ ሰዎች ፡ ፍርዱ ፡ ፈጥ
ነው ፡ ይጠፋሉና ፡ የሰው ፡ ገንዘብ ፡ ቀምተው ፡
ቤታቸውን ፡ ለሚሠሩ ፡ ሰዎች ፡ ወዮላቸው ።
በባለጠግነታችሁ ፡ ላይ ፡ ታምናችኋልና ፡ ከባ ፰፣
ለጠግነታችሁም ፡ ትለያላችሁና ፡ እናንተ ፡ ባለ
ጠጎች ፡ ወዮላችሁ ።
እግዚአብሔርን ፡ በባለጠግነታችሁ ፡ ወራት ፡ ፱፣
አላሰባችሁትምና ፡ እናንተስ ፡ ስድብን ፡ በደል
ንም ፡ ሠራችኋት ፡ ደም ፡ ለሚፈስበት ፡ ጨለ
ማም ፡ ለሚደረግበት ፡ ጽኑ ፡ ፍርድም ፡ ለሚፈ
ረድበት ፡ ዕለተ ፡ ምጽአትም ፡ የተዘጋጃችሁ ፡
ሆናችሁ ።
የፈጠራችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲያጠፋችሁ ፡ ፲፣
በናንተም ፡ ጥፋት ፡ ላይ ፡ ይቀርታው ፡ እንዳይ
ደረግላችሁ ፡ እኔም ፡ እንደዚህ ፡ ብዬ ፡ እነግራ
ችኋለሁ ።
እናንተንም ፡ የፈጠረ ፡ እግዚአብሔር ፡ በናንተ ፡ ፲፩፣
ጥፋት ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፡ የናንተም ፡ መምሮቻ
ችሁም ፡ በነዚያ ፡ ወራት ፡ ሕገ ፡ እግዚአብሔ
ርን ፡ ለዘነጉ ፡ ሰዎችና ፡ ለኃጥአን ፡ ስድብ ፡ ይሆ
ናሉ ።
ዓይኖቼ ፡ ውሀን ፡ የቋጠሩ ፡ ደመናዎችን ፡ ይሆኑ ፡ ፲፪፣
ዘንድ ፡ በናንተም ፡ ላይ ፡ አለቅስ ፡ ዘንድ ፡ ውሀ
ንም ፡ እንደ ፡ ቋጠረ ፡ ደመና ፡ እንባዬን ፡ አፈስ ፡
ዘንድ ፡ ከልቡናዬም ፡ ኀዘን ፡ አርፍ ፡ ዘንድ ፡ ላይ
ኖቼ ፡ ማን ፡ በሰጠኝ ፡ ነበር ።
ክፋትንና ፡ ስድብን ፡ ታደርጉ ፡ ዘንድ ፡ አድርጉ ፡ ፲፫፣
ብሎ ፡ ማን ፡ አስተማራችሁ ፡ እግዚአብሔርን ፡
ኃጥአን ፡ እናንተን ፡ ቍርጥ ፡ ፍርድ ፡ ያገኛች
ኋል ።
እንደ ፡ ወደዳችሁ ፡ በነሱ ፡ ላይ ፡ ፍርድን ፡ ታደ ፲፬፣
ርጉባቸው ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዳግመኛ ፡
በጃችሁ ፡ ይጥሏቸዋልና ፡ ወዳጆቼ ፡ ጻድቃን ፡
ከኃጥአን ፡ የተነሣ ፡ አትፍሩ ።
እንዳትፈቱ ፡ ሁናችሁ ፡ የማይገባ ፡ ግዝትን ፡ ፲፭፣
ለምትገዝቱ ፡ ለናንተ ፡ ወዮላችሁ ፡ ስለ ፡ ኃጢ
አታችሁም ፡ ድኅነት ፡ ከናንተ ፡ ራቀ ።
እንደ ፡ ሥራችሁ ፡ መጠን ፡ ፍዳውን ፡ ትቀበላላ ፲፮፣
ችሁና ፡ ለባልንጀራችሁ ፡ ክፉ ፡ ምላሽ ፡ ለምት
መልሱ ፡ ለናንተ ፡ ወዮላችሁ ።
በሠራችሁት ፡ ሥራ ፡ ፈጥናችሁ ፡ ትጠፉላች ፲፯፣
ሁና ፡ ሐሰት ፡ ለምትመሰክሩ ፡ ለበደልም ፡ ለም
ትገቧት ፡ ለናንተ ፡ ወዮላችሁ ።
ደጋግ ፡ ሰዎችን ፡ አስወጥታችሁ ፡ ትሰዷቸዋላ ፲፰፣
ችሁና ፡ እናንተም ፡ በነሱ ፡ እጅ ፡ ትወድቃላች
ሁና ፡ ከሠራችሁትም ፡ ግፍ ፡ የተነሣ ፡ ትሰደዳ
ላችሁና ፡ የነሱም ፡ ፍዳ ፡ በናንተ ፡ ይጸናልና ፡
ለናንተ ፡ ለኃጥአን ፡ ወዮላችሁ ።
ጠላቶቻችሁ ፡ ኃጥአን ፡ ከፊታችሁ ፡ ፈጥነው ፡ ፲፱፣

እንዲጠፉ ፡ እንደ ፡ ወደዳችሁ ፡ ሥልጣንም ፡
በነሳቸው ፡ እንዲደረግ ፡ ወዳጆቼ ፡ ጻድቃን ፡
ይህንን ፡ ተስፋ ፡ አደረጉ ።
፳፡ ኃጥአን ፡ መከራ ፡ በሚቀበሉበትም ፡ ቀን ፡ የና
ንተ ፡ ልጆች ፡ እንዳሞሮች ፡ ተነሥተው ፡ ከፍ ፡
ከፍ ፡ ይላሉ ።
፳፩፡ በታችሁም ፡ ከጥንብ ፡ አሞራ ፡ በታ ፡ ይልቅ ፡
ይርቃል ፡ ወጥታችሁም ፡ ወደ ፡ ቀበሮ ፡ ጉድ
ጓድ ፡ ከመዐኞችም ፡ ፊት ፡ የተነሣ ፡ እንደ ፡
ሽኮኮ ፡ ለዘላለሙም ፡ ወደ ፡ ገደል ፡ ጥግ ፡ ትገባ
ለች ።
፳፪፡ በናንተም ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ሥራቸውን ፡ ይሠራሉ ፡
ይህ ፡ ኃጢአታችሁ ፡ በናንተ ፡ ምስክር ፡ ይሆን
ባችኋል ፡ እንጂ ፡ እናንተ ፡ እንደነሱ ፡ አትሆ
ኑም ፡ ለወንድሞቻችሁም ፡ ከኃጥአንም ፡ ጋራ ፡
አንድ ፡ ሆናችሁ ፡ እንደ ፡ ሄለይም ፡ ቃላቸውን ፡
አቅጥነው ፡ ያለቅሳሉ ።
፳፫፡ ይህ ፡ መከራው ፡ ለናንተ ፡ ድኅነት ፡ ይሆንላች
ኋልና ፡ የበራም ፡ ብርሃን ፡ ለናንተ ፡ ያበራላች
ኋልና ፡ ከሰማይም ፡ ዕረፍት ፡ የሚደረግበትን ፡
ቃል ፡ ትሰማላችሁና ፡ መከራ ፡ የምትቀበሉ ፡
ጻድቃን ፡ እናንተ ፡ ግን ፡ አትፍሩ ።
፳፬፡ ባለጸግነታችሁ ፡ ደጋግ ፡ ሰዎችን ፡ ያስመስላች
ኋልና ፡ እናንተ ፡ ክፉዎች ፡ ኃጥአን ፡ ወዮላችሁ ፡
ልቡናችሁ ፡ ግን ፡ እናንተ ፡ በደለኞች ፡ እንደ ፡
ሆናችሁ ፡ ይዘልፋችኋል ። (ያውቅባችኋል ፡)
፳፭፡ ይህም ፡ ነገር ፡ በናንተ ፡ ለክፋታችሁ ፡ መታስ
ቢያ ፡ ምስክር ፡ ይሆናል ፡ አለ ።
፳፮፡ ያፈራውን ፡ ስንዴ ፡ የምትበሉ ፡ ከላምም ፡ ጡት ፡
የተገኘ ፡ ወተቱንም ፡ የምትጠጡ ፡ የተጥረዱ
ትንም ፡ ሰዎች ፡ በኃይላችሁ ፡ የምትረግጧ
ቸው ፡ ለናንተ ፡ ወዮላችሁ ።
፳፯፡ የኃጢአታችሁን ፡ ፍዳ ፡ ፈጥናችሁ ፡ ትቀበላላ
ችሁና ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ ውኃን ፡ ለምትጠጡ ፡ ሰዎች ፡
ወዮላችሁ ፡ የሕይወት ፡ መገኛ ፡ ሕጉን ፡ ትታ
ችኋልና ፡ ፈጽማችሁ ፡ ትጠፋላችሁ ።
፳፰፡ በደልን ፡ ተንኰልን ፡ ስድብን ፡ ለምትሠሩ ፡
ለናንተ ፡ ወዮላችሁ ፡ ይህም ፡ በናንተ ፡ የክፋታ
ችሁ ፡ መታሰቢያ ፡ ይሆናል ።
፳፱፡ የምትጠፉበት ፡ ቀን ፡ ትመጣለችና ፡ ደጉን ፡
ሰው ፡ በኃይላችሁ ፡ ራስ ፡ ራሱን ፡ ለምትቀጠ
ቅጡት ፡ ለናንተ ፡ ለኃይለኞች ፡ ወዮላችሁ ።
፴፡ በነዚያ ፡ ወራቶች ፡ ለደጋግ ፡ ሰዎች ፡ በናንተ ፡
በተፈረደባችሁ ፡ ቀን ፡ ደጋጎችና ፡ ብዙዎች ፡
ወራቶች ፡ ይመጣሉ ፡ አለ ።

## ምዕራፍ ፡ ፻፬ ።

፩፡ ኃጥአን ፡ ለስድብ ፡ እንዲሆኑ ፡ ግፍም ፡ በሠ
ሩበት ፡ ቀን ፡ እንዲጠፉ ፡ ወዳጆቼ ፡ ጻድቃን ፡
እመኑ ።
፪፡ እግዚአብሔር ፡ የናንተን ፡ ጥፋት ፡ ያስባልና ፡
በሰማይም ፡ ያሉ ፡ መላእክት ፡ በናንተ ፡ ጥፋት ፡
ላይ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋልና ፡ ይህ ፡ በደግነታችሁ ፡
የታወቀ ፡ ይሆንላችኋል ።
ኃጥአን ፡ ምን ፡ ታደርጉ ፡ ዘንድ ፡ አላችሁ ፡ የጻ ፫፡
ድቃን ፡ ጸሎታቸው ፡ ዋጋ ፡ ሊያሰጥ ፡ በሰማ
ችሁ ፡ ጊዜ ፡ ፍርድ ፡ በሚፈረድበት ፡ በዚያች ፡
ቀንስ ፡ ወዴት ፡ ትሸሻላችሁ ።
በነዚያም ፡ ወራቶች ፡ የቅዱሳን ፡ ልመናቸው ፡ ፬፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ትደርሳለች ፡ በናንተ ፡
ግን ፡ የሚፈረድባችሁ ፡ ወራት ፡ ይደርስባችኋል ።
በግፋችሁ ፡ የሠራችሁትም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በከ ፭፡
በረና ፡ በገነነ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ይነበ
ባል ፡ ፊታችሁም ፡ በመከራው ፡ ያፍራል ፡ በግፍ ፡
የጸና ፡ ሥራችሁም ፡ ሁሉ ፡ ይጠፋል ።
በየብስና ፡ በባሕር ፡ መካከል ፡ ያላችሁ ፡ የክፉ ፮፡
ዎች ፡ ሰዎችም ፡ ስም ፡ አጠራራቸው ፡ በናንተ ፡
የተጠራባችሁ ፡ ኃጥአን ፡ ለናንተ ፡ ወዮላችሁ ።
በውነት ፡ ያይደለ ፡ ወርቅና ፡ ብርን ፡ የምትሰበ ፯፡
ስቡ ፡ ባለጸግነትን ፡ አገኘን ፡ ገንዘቡም ፡ በዛልን ፡
የወደድነውንም ፡ ሁሉ ፡ ገዛን ፡ የምትሉ ፡ ሰዎች ፡
ለናንተ ፡ ወዮላችሁ ።
ብሩን ፡ ሰብስበናልና ፡ በሳጥኖቻችንም ፡ መልተ ፰፡
ናልና ፡ በቤታችንም ፡ ያሉ ፡ አራሾች ፡ እንደ ፡
ውሀ ፡ በገዙተውልናልና ፡ አሁንም ፡ ያሰብነውን ፡
ሁሉ ፡ እናድርግ ፡ ለምትሉ ፡ ለናንተ ፡ ወዮላ
ችሁ ።
ከናንተ ፡ ፈጥኖ ፡ ይጠፋል ፡ እንጂ ፡ ባለጠግነት ፡ ፱፡
አይኖርላችሁምና ፡ አሰታችሁ ፡ እንደ ፡ ውሀ ፡
ይበዛል ።
ይህን ፡ ሁሉ ፡ በግፍ ፡ ሰብስባችሁታልና ፡ እና ፲፡
ንተ ፡ ግን ፡ ለጽኑ ፡ ጥፋት ፡ ትሰጣላችሁ ።
በዚህም ፡ ዓለም ፡ ብዙ ፡ ነገርን ፡ ታያላችሁና ፡ ፲፩፡
ዛሬም ፡ ሰነፎችና ፡ ብልሆች ፡ ለምትሆኑ ፡ ለና
ንተ ፡ እነግራችኋለሁ ።
እናንተ ፡ ወንዶቼ ፡ ከሴቶች ፡ ይልቅ ፡ እናንተ ፡ ፲፪፡
ጌጡን ፡ ታጌጣላችሁና ፡ ይልቁን ፡ ከድንግሊቱ ፡
ይልቅ ፡ ብዙ ፡ መልክ ፡ ያለው ፡ ጌጥን ፡ ታደርጋ
ላችሁና ።
በመንግሥት ፡ በገናንነት ፡ በሥልጣን ፡ ያለን ፡ ፲፫፡
ይመስላችኋል ፡ በወርቅና ፡ በብር ፡ በነጭ ፡
ሐርም ፡ የከበርን ፡ ይመስላችኋል ።
መብሎችም ፡ እንደ ፡ ውሀ ፡ በገዙተው ፡ በፊታ ፲፬፡
ቸው ፡ ይቀርባሉ ፡ ስለዚህም ፡ ነገር ፡ ጥበብና ፡
ትምህርት ፡ የላቸውም ።
በዚህም ፡ በመብሉና ፡ በመጠጡ ፡ ገንዘቦቻቸው ፡ ፲፭፡
ከክብራቸውና ፡ ከጌትነታቸውም ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡
አንድ ፡ ሆነው ፡ ይጠፋሉ ።
በስድብ ፡ በችጋር ፡ በጽኑ ፡ በቀልም ፡ ሁነው ፡ ፲፮፡
ሊኖሩ ፡ ነፍሳቸው ፡ ወደ ፡ እሳት ፡ ጕድጓድ ፡
ትወድቃለች ፡ ( ገሃነም ፡ ነው ) ።
ኃጥአን ፡ ተራራው ፡ በባሕርዩ ፡ ተገዥ ፡ እንዳል ፲፯፡
ነበረ ፡ እንግዲህም ፡ ወዲህ ፡ እንዳይሆን ፡ ክረብ
ታይቱም ፡ ለሴት ፡ ሴት ፡ ባሪያ ፡ እንዳይደሉ ፡
ለናንተ ፡ ነገርኋችሁ ።
አዳምና ፡ ሔዋን ፡ ከራሳቸው ፡ አንቅተው ፡ ፲፰፡
ሠሯት ፡ እንጂ ፡ አሁን ፡ እንደ ፡ ተናገርሁት ፡
ኃጢአትም ፡ ወደዚህ ፡ ዓለም ፡ የባሕርይ ፡ ሁና ፡

አልተላከችም ፡ እሷንም ፡ የሠሯት ፡ ሰዎች ፡
ለጽኑ ፡ መርገም ፡ ይሆናሉ ፡ ( ሑሩ ፡ ይባላሉ ) ።
፲፱ በጅዋ ፡ በሠራችው ፡ ሥራ ፡ ልጅ ፡ ሳትወልድ ፡
ትሞታለች ፡ እንጂ ፡ ለሴትም ፡ መምከን ፡ አል
ተሰጣትም ፡ ነበር ።
፳ ኃጥአን ፡ ክፉ ፡ ሠራችሁ ፡ ሁሉ ፡ በሰማይ ፡ እንደ ፡
ተገለጠ ፡ ፈጽሞም ፡ የተሠወረ ፡ የግፍ ፡ ሥራም ፡
እንደሌላችሁ ፡ በገናናና ፡ በከበረ ፡ ስሙ ፡ ምዬ ፡
ነገርኋችሁ ።
፳፩ በሰውነታችሁ ፡ በልቡናችሁም ፡ የሚሠወርላ
ችሁ ፡ አታስመስሉት ፡ በሰማይ ፡ በእግዚአብ
ሔር ፡ ፊት ፡ ይጻፍ ፡ ዘንድ ፡ እንዳለው ፡ በየቀኑ ፡
የሠራችሁትን ፡ ሁሉ ፡ ፈጽማችሁ ፡ አታውቁ
ምና ፡ በልቡናችሁ ፡ ይሠወርልናል ፡ አትበሉ ።
፳፪ ፍርድ ፡ እስከሚፈረድበት ፡ እስከ ፡ ዕለተ ፡ ምጽ
አት ፡ ድረስ ፡ የበደላችሁት ፡ በደል ፡ በየቀኑ ፡
ሁሉ ፡ እንዲጻፍባችሁ ፡ ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ ታው
ቃላችሁ ።
፳፫ በስንፍናችሁ ፡ ትጠፋላችሁና ፡ መምራንንም ፡
አትሰሟቸውምና ፡ በጎ ፡ ነገርም ፡ አታገኙችሁ
ምና ፡ እናንት ፡ ሰነፎች ፡ ወዮላችሁ ።
፳፬ አሁንም ፡ ጥፋት ፡ ለታዘዘባት ፡ ቀን ፡ እናንተ ፡
የተዘጋጃችሁ ፡ እንደሆናችሁ ፡ እወቁ ፡ ተፈር
ዶባችሁ ፡ ወደገሃነም ፡ ትሄዳላችሁ ፡ እንጂ ፡ ኃጥ
አን ፡ እንድናለን ፡ ብላችሁ ፡ ተስፋ ፡ አታድርጉ ።
፳፭ ጽኑ ፡ ፍርድ ፡ ለሚፈረድበት ፡ ቀን ፡ መከራም ፡
በታዘዘበት ፡ በሰውነታችሁም ፡ ታላቅ ፡ ጉስቁ
ልና ፡ በታዘዘበት ፡ ቀን ፡ ለጥፋት ፡ ተዘጋጅታ
ችኋልና ፡ ምግባርን ፡ ስላላወቃችሁ ፡ በነፍስ ፡
ትሞታላች ።
፳፮ ክፉ ፡ ሥራን ፡ የምትሠሩ ፡ ብርንዶንም ፡ የም
ትበሉት ፡ እናንት ፡ ልበ ፡ ድንጋዎች ፡ ወዮላ
ችሁ ፡ ገናና ፡ እግዚአብሔር ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡
አብዝቶ ፡ የፈጠረው ፡ ፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ ያመረ ፡
ነው ፡ እያላችሁ ፡ በተድላ ፡ በደስታ ፡ ትበላላ
ችሁ ፡ ትጠጣላችሁ ፡ ትጠግባላችሁ ፡ እናንተ ፡
ከወዴት ፡ አግኝታችሁት ፡ ነው ፡ አንድነትም ፡
የላችሁም ።
፳፯ የበደልን ፡ ሥራ ፡ ለምትወዷት ፡ ለናንተ ፡ ወዮ
ላችሁ ፡ በጎይቱንስ ፡ ለምን ፡ ትመኗታላችሁ ።
፳፰ በጻድቃንም ፡ እጆች ፡ አልፋችሁ ፡ ትያዙ ፡
ዘንድ ፡ አደላችሁ ፡ እወቁ ፡ አንገቶቻችሁንም ፡
ቆርጠው ፡ ይገሏችኋል ፡ ከዚያም ፡ አስቀድ
መው ፡ አይራሩላችሁም ።
፳፱ ለናንተ ፡ መቃብር ፡ አይቆፍሩላችሁምና ፡ በጻ
ድቃን ፡ መከራ ፡ ደስ ፡ ለሚላችሁ ፡ ለናንተ ፡
ወዮላችሁ ።
፴ የድኅነት ፡ አለኝታ ፡ አይደረግላችሁምና ፡ የመ
ምህራንን ፡ ነገር ፡ ለምትንቁ ፡ ለናንት ፡ ወዮላ
ችሁ ።
፴፩ ሐሰት ፡ ነገራቸውን ፡ ይሰሟት ፡ ዘንድ ፡ ስንፍና
ቸውንም ፡ እንዳይዘነጓት ፡ እነሱ ፡ አሰታቸውን ፡
ይጽፉሉና ፡ ሕጉን ፡ የዘነጉ ፡ ሰዎች ፡ ነገርንና ፡
የአሰትን ፡ ነገር ፡ ለምትጽፉ ፡ ለናንት ፡ ወዮላ
ችሁ ።
አይዘገዩም ፡ ፈጥነው ፡ ይሞታሉ ፡ እንጂ ፡ ፍቅር ፡ ፴፪
አንድነት ፡ አይደረግላቸውም ።
ክፉ ፡ እርጂና ፡ ለምታረጁ ፡ ሰዎች ፡ ወዮላችሁ ፡ ፴፫
የሐሰቱንም ፡ ነገር ፡ ፈጽመው ፡ ያከብራሉ ፡
በዚህም ፡ ሥራችሁ ፡ ጠፉችሁ ፡ ድኅነት ፡ በጎም ፡
ነገር ፡ የላችሁም ።
የቀኑ ፡ ነገሮችንም ፡ ለምትለዋውጧቸው ፡ ለና ፴፬
ንተ ፡ ወዮላችሁ ፡ ለዘላለም ፡ ጸንቶ ፡ የሚኖረው
ንም ፡ ሥርዓት ፡ ይለውጣሉ ፡ ራሳቸውንም ፡ ኃጢ
አተኞች ፡ ያስደረጉ ፡ ሰዎች ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡
ይጠፉ ፡ ዘንድ ፡ አላቸው ።

ምዕራፍ ፡ ፴፰ ።

በነዚያም ፡ ወራቶች ፡ ጻድቃን ፡ ለበጐነታ ፩
ችሁ ፡ መታሰቢያ ፡ ሊሆን ፡ የለመናችሁትን ፡
ዋጋ ፡ ትቀበሉ ፡ ዘንድ ፡ ተዘጋጁ ።
በልዑል ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ ለክፋታቸው ፡ ፪
መታሰቢያ ፡ አድርገው ፡ ኃጥአን ፡ ኃጢአታቸ
ውን ፡ እንዲያኖሩት ፡ እናንተም ፡ በመላእክት ፡
ፊት ፡ ለበጐነታቸው ፡ ምስክር ፡ አድርጋችሁ ፡
ክብሮቻችሁን ፡ አኖራችኋቸው ።
በነዚያም ፡ ወራቶች ፡ አሕዛብ ፡ ይተዋወከሉ ፡ ፫
ጥፋትም ፡ በታዘዘባት ፡ ቀን ፡ የአሕዛብ ፡ ዘመ
ዶች ፡ ይነሣሉ ።
በነዚያም ፡ ወራቶች ፡ የተቸገሩ ፡ ሰዎች ፡ ተሰ ፬
ደው ፡ ይወጣሉ ፡ ልጆቻቸውንም ፡ አሕዛብ ፡
ይነጥቋቸዋል ፡ ልጆቻቸውንም ፡ እየወጉ ፡ ይጥ
ሏቸዋል ።
ከነሱም ፡ የተነሣ ፡ ልጆቻቸው ፡ ውራጅ ፡ ይሆ ፭
ናሉ ፡ የናታቸውንም ፡ ጡት ፡ ሲጠቡ ፡ ልጆቻ
ቸውን ፡ እየወጉ ፡ ይጥሏቸዋል ።
ወደነሱም ፡ በፍቅር ፡ አይመለሱም ፡ ለሚወዷ ፮
ቸው ፡ ልጆቻቸው ፡ አይራሩላቸውም ።
የማይገታ ፡ ደም ፡ ለሚፈስባት ፡ ቀን ፡ ኃጢአት ፡ ፯
ተዘጋጅታለችና ፡ ለኃጥአን ፡ እኔ ፡ ዳግመኛ ፡ እነ
ግራችኋለሁ ።
ለድንጋይም ፡ ይሰግዳሉ ፡ የብሩና ፡ የወርቁን ፡ ፰
የሸክላውንና ፡ የንጨቱንም ፡ ምስል ፡ የሚሠሩ ፡
ናቸው ።
ለረከሱ ፡ ለረቂቃን ፡ ለክፉዎችም ፡ ለግዙፋን ፡ ፱
አጋንንት ፡ ለጣዖቱም ፡ ሁሉ ፡ ለመስጊድም ፡
ሁሉ ፡ ይሰግዳሉ ።
ከነሳቸውም ፡ ረድኤት ፡ ሁሉ ፡ አይገኝም ፡ ስለ ፡ ፲
ልቡናቸውም ፡ ድንቍርና ፡ ከሥላሴ ፡ ልቡና ፡
ይዘነጋሉ ፡ በልቡናቸው ፡ ፍርሃት ፡ የልቡና
ቸው ፡ ዓይኖች ፡ በድንቍርና ፡ ይያዛሉ ።
ሥራቸውን ፡ ሁሉ ፡ በሰት ፡ ሠርተዋልና ፡ ለድን ፲፩
ጋዩም ፡ ሰግደዋልና ፡ ፈጥነውም ፡ ይጠፋሉና ፡
ሕልማቸውን ፡ አየን ፡ በማለታቸው ፡ ሕጉን ፡
ይዘነጋሉ ፡ መከራውንም ፡ ይፈራሉ ።
በነዚያም ፡ ወራቶች ፡ የጥበብን ፡ ነገር ፡ የሚቀ ፲፪
በሉ ፡ የሚወዷትም ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ የተደነቁ ፡
ሰዎች ፡ ናቸው ።

፲፫፤ የልዑል ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ሥራዎች ፡ ይሠ
ሯቸዋል ፡ በውነተኛም ፡ ሥራዎች ፡ ጸንተው ፡
ይኖራሉ ፡ እነሱ ፡ ይድናሉና ፡ ሕጉን ፡ እንደ ፡
ዘነጉ ፡ ሰዎች ፡ ሕጉን ፡ አይዘነጉም ።
፲፬፤ በሲኦል ፡ ትጠፋላችሁና ፡ ለወንድማችሁ ፡ ክፉ
ውን ፡ ነገር ፡ አብዝታችሁ ፡ የምትሠሩ ፡ ለእና
ንተ ፡ ወዮላችሁ ።
፲፭፤ በሱ ፡ ትጠፋላችሁና ፡ ተንኰልንና ፡ ኃጢአትን ፡
መሠረት ፡ ንፍገትን ፡ የምትሠሩ ፡ በዚህም ፡
ዓለም ፡ እግዚአብሔርን ፡ የምትአሳዝኑ ፡ ሰዎች ፡
ወዮላችሁ ።
፲፮፤ በድኃ ፡ ገንዘብ ፡ ቤታችሁን ፡ የምትሠሩ ፡ እናንተ ፡
ወዮላችሁ ፡ ሥራቸውም ፡ ሁሉ ፡ ውብ ፡ ነው ፡
የኃጢአትም ፡ የሚሠራበት ፡ ደንጊያ ፡ ነው ፡
አንድነትም ፡ እንደሌላችሁ ፡ እኔ ፡ እነግራችኋ
ለሁ ።
፲፯፤ ለዘለዓለሙ ፡ የሚኖር ፡ የአባቶቻቸው ፡ ርስትና ፡
ድንበርን ፡ ለሚያፈርሱ ፡ ሰዎች ፡ ወዮላቸው ፡
ለነሱ ፡ ዕረፍተ ፡ ነፍስ ፡ አይደረግምና ፡ ልቡና
ቸውንም ፡ ወደ ፡ ጣዖቱ ፡ ይወስዱታል ።
፲፰፤ በደልን ፡ የምትሠሪት ፡ ግፍንም ፡ ለምትረ
ዱት ፡ ለናንተ ፡ ወዮላችሁ ፡ ጌትነታችሁን ፡ ያጠ
ፉዋልና ፡ በልቡናችሁም ፡ ክፉትን ፡ ያሳድርብ
ችኋልና ፡ ጽኑ ፡ ፍርድ እስከሚፈረድበት ፡ እስከ ፡
ዕለተ ፡ ምጽአት ፡ ድረስ ፡ ባልንጀሮቻችሁን ፡
ለምትገሉ ፡ ሰዎች ፡ ወዮላችሁ ።
፲፱፤ ሁላችሁንም ፡ በሰይፍ ፡ ያጠፉችሁ ፡ ዘንድ ፡
ረቂቅ ፡ ቍጣን ፡ አመጣባችሁ ፡ ደናግልና ፡ ሕጋ
ውያንም ፡ ሁሉ ፡ ኃጢአታችሁን ፡ ያስባሉ ።
፳፤ በነዚያም ፡ ወራቶች ፡ አባቶች ፡ ከልጆቻቸው ፡
ጋር ፡ በንድ ፡ በታ ፡ ተቀራደው ፡ ያልቃሉ ።
፳፩፤ ሰው ፡ ልጁን ፡ ከመግደል ፡ የልጅ ፡ ልጁንም ፡
ከመግደል ፡ በመራራት ፡ እጁን ፡ አይከለክል
ምና ፡ ከነሱ ፡ ደም ፡ እንደ ፡ ፈሳሽ ፡ ውኃ ፡ እስቲ
ፈስ ፡ ድረስ ፡ ደርሶ ፡ ወንድሞች ፡ ከወንድሞቻ
ቸው ፡ ጋራ ፡ በሞት ፡ ይጠፋሉ ።
፳፪፤ ኃጢአተኛው ፡ የከበረ ፡ ታላቅ ፡ ወንድሙን ፡
ከመግደል ፡ እጁን ፡ አይከለክልም ፡ ጎሕም ፡
ከቀደደ ፡ ጀምሮ ፡ ፀሐይ ፡ እስኪገባ ፡ ድረስ
ይዋጋሉ ።
፳፫፤ ፈረስ ፡ የኃጥአን ፡ ደም ፡ እስከ ፡ አቢያጉሱ ፡
ድረስ ፡ እያማታው ፡ ይሄዳል ፡ ሠረገላ ፡ ግን ፡
እስከ ፡ ራሷ ፡ ድረስ ፡ ትሰጥማለች ።
፳፬፤ በነዚያም ፡ ወራቶች ፡ አለቆች ፡ ወደሚሠሩት ፡
በታ ፡ ይወርዳሉ ።
፳፭፤ ኃጢአትን ፡ የሚረዱት ፡ ሰዎችንም ፡ ሁሉ ፡
ወደ ፡ አንዱ ፡ በታ ፡ ይመልሷቸዋል ።(ገሃነም፡)
፳፮፤ በኃጥአን ፡ ሁሉ ፡ ፍርድ ፡ ይፈረድ ፡ ዘንድ ፡ በዚ
ያች ፡ ቀን ፡ እግዚአብሔር ፡ በመዓት ፡ ይነሣል ።
፳፯፤ ከከበሩ ፡ መላእክትም ፡ በደናግልና ፡ በሕጋው
ያን ፡ ላይ ፡ ጠባቂዎችን ፡ ይሰጣል ፡ እነሱም ፡
ከፋት ፡ ሁሉ ፡ ኃጢአትም ፡ ሁሉ ፡ ጨርሶ ፡ እስ
ኪጠፉ ፡ ድረስ ፡ እንደ ፡ ዓይን ፡ ብሌኔ ፡ ይጠብቋ
ቸዋል ።

ቢተኙም ፡ ብዙ ፡ እንቅልፍን ፡ ይተኛሉ ፡ የሚ ፳፰፤
ፈሩትም ፡ ነገር ፡ የላቸውም ።
በዚያም ፡ ወራት ፡ ብልሆች ፡ ሰዎች ፡ እውነተኛ ፡ ፳፱፤
ነገርን ፡ ያያሉ ፡ በዚህም ፡ ዓለም ፡ ያሉ ፡ ሰዎች ፡
በዚች ፡ መጽሐፍ ፡ የተጻፈውን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡
ልብ ፡ ያደርጋሉ ፡ ባለጸግነታቸውም ፡ ኃጢአት ፡
ሠርተው ፡ በሚጠፉበት ፡ ጊዜ ፡ ማዳናቸውን ፡
እንዳይችል ፡ ያውቃል ።
ጽኑ ፡ መከራ ፡ በምታደርጉበት ፡ ቀን ፡ ጻድቃ ፴፤
ንን ፡ በስጨንቃችኋቸው ፡ ጊዜ ፡ ኃጥአን ፡ ወዮ
ላችሁ ፡ በእሳትም ፡ ታቃጥሏቸዋላችሁ ፡ እናን
ተም ፡ እንደ ፡ ሥራችሁ ፡ ፍዳውን ፡ ትቀበላላ
ችሁ ።
ክፉውን ፡ ነገር ፡ ልብ ፡ ታደርጉ ፡ ዘንድ ፡ የም ፴፩፤
ትተጉ ፡ ልባችሁ ፡ ግልብጥብጥ ፡ ላለ ፡ ለናንተ ፡
ወዮላችሁ ፡ ፍራት ፡ ያገኛችሁ ፡ ዘንድ ፡ አላችሁ ፡
የሚረዳችሁም ፡ ወዳጅ ፡ የለም ።
በፋችሁ ፡ በተናገራችሁ ፡ ነገር ፡ ላይ ፡ ሕግንም ፡ ፴፪፤
በዘነጋችሁበት ፡ በጃችሁም ፡ ሥራ ፡ ላይ ፡ በገሃ
ነም ፡ ትቃጠላላችሁና ፡ ኃጥአን ፡ ለናንተ ፡ ወዮ
ላችሁ ።
ጨረቃንና ፡ ፀሐይን ፡ ከከቦችንም ፡ ከማምለክ ፴፫፤
ቸው ፡ የተነሣ ፡ ስለ ፡ ኃጢአታችሁ ፡ መላእክት ፡
በሰማይ ፡ ሥራችሁን ፡ እንዲመረምሩ ፡ አሁ
ንም ፡ እወቁ ።
በወዳጆቹ ፡ በጻድቃን ፡ ዘንድ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ፴፬፤
ጽኑ ፡ መቻያን ፡ ታደርጉባቸዋላችሁና ፡ ጉሙ
ንና ፡ ደመናውን ፡ ሁሉ ፡ ዝናቡንና ፡ ጠሉንም ፡
በናንተ ፡ ያዳኝባችኋል ፡ ወደናንተ ፡ እንዳይወ
ርዱ ፡ ከናንተ ፡ የተነሣ ፡ ሁሉ ፡ ይከለከላሉና ፡
በኃጢአታችሁም ፡ መውረድን ፡ አያስቡምና ።
አሁንም ፡ ዝናብ ፡ ወደናንተ ፡ መውረድን ፡ እን ፴፭፤
ዳይከለከል ፡ ጠልም ፡ ከናንተ ፡ ብርንና ፡ ወር
ቅን ፡ ተቀብሎ ፡ ይወርድ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እጅ ፡
መንሻ ፡ ስጡ ።
ውርጭ ፡ ቍማም ፡ በናንተ ፡ ቢወድቅባችሁ ፡ የነ ፴፮፤
ሱም ፡ ቅዝቃዜ ፡ ቢደረግባችሁ ፡ ዋጉን ፡ የሚ
ያመጡ ፡ ነፋሶች ፡ ሁሉ ፡ ቢታዘዙባችሁ ፡ የነ
ዚህ ፡ ሁሉ ፡ ጭንቅነትም ፡ ያገኛችሁ ፡ በነዚያ ፡
ወራት ፡ በነሱ ፡ ፊት ፡ መቆም ፡ አይቻላችሁም ።

## ምዕራፍ ፡ ፴፱ ።

በደብር ፡ ቅዱስ ፡ የነበራችሁ ፡ እናንተ ፡ ሁሉ ፡ ፩፤
ሰማያዊ ፡ ሕግን ፡ ተረዱት ፡ የእግዚአብሔር
ንም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ መርምሩ ፡ በፊቱ ፡ ክፉ ፡
ነገርን ፡ እንዳትሠሩ ፡ ከሱ ፡ የተነሣ ፡ ፍሩ ።
የሰማይ ፡ ደጃፍን ፡ ቢዘጋ ፡ ዝናቡን ፡ ጠሉንም ፡ ፪፤
ወደዚህ ፡ ዓለም ፡ እንዳይወርድ ፡ በናንተ ፡ ምክ
ንያት ፡ ቢከለክለው ፡ ምን ፡ ታደርጉ ፡ ዘንድ ፡
አላችሁ ።
መዓቱን ፡ በናንተ ፡ በሥራችሁም ፡ ሁሉ ፡ ቢያ ፫፤
መጣባችሁ ፡ እናንተ ፡ እሱን ፡ የምትለምኑት ፡
አይደለምን ፡ አለ ።
በቸርነቱ ፡ ላይ ፡ ታላላቅ ፡ የጸኑ ፡ ነገሮችንም ፡ ፬፤

ትናገራላችሁና ፡ ከሱ ፡ ጋር ፡ ፍቅር ፡ አንድነት ፡
የላችሁም ።
፭ ከማዕበል ፡ ከሞገዱ ፡ የተነሣ ፡ እንዲተዋወኩ ፡
መርከቦቻቸውም ፡ ከነፋሶች ፡ የተነሣ ፡ እንዲነ
ዋወጡ ፡ እንዲጨነቁ ፡ በመርከብ ፡ ተጭነው ፡
የሚሄዱ ፡ ነገሥታትን ፡ አታዋቸውምን ፡ አለ ።
( ነጋድያን ። )
፮ ያማረ ፡ ገንዘባቸው ፡ ሁሉ ፡ ከነሱ ፡ ጋር ፡ አብሯ
ቸው ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ይወጣልና ፡ ስለዚህም ፡
ነገር ፡ ይፈራሉ ።
፯ ባሕር ፡ የምትውጣቸው ፡ በሷም ፡ የሚጠፉ ፡
መስሏቸዋልና ፡ በልቡናቸው ፡ በጎ ፡ ነገርን ፡ አያ
ስቡም ፡ ባሕር ፡ ሁሉ ፡ ውሀዎቿም ፡ ሁሉ ፡ መነዋ
ወጧም ፡ ሁሉ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሥራ ፡ ነውና ።
፰ እሱ ፡ ሥራዋን ፡ ሁሉ ፡ ውሀዎቿንም ፡ ሁለመ
ናዋን ፡ ሁሉ ፡ በሻዋ ፡ ወስኗልና ።
፱ ቍጣውን ፡ ፈርታ ፡ ትደርቃለች ፡ ዓሣዎቿም ፡
ሁሉ ፡ ይሞታሉ ፡ በሷም ፡ ያለው ፡ ሁሉ ፡
ይሞታሉ ።
፲ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ያላችሁ ፡ እናንተ ፡ ኃጥአን ፡
ግን ፡ አትፈሩም ፡ ምድርና ፡ ሰማይን ፡ በነሱ ፡
ያለውንም ፡ ሁሉ ፡ የፈጠረ ፡ እሱ ፡ አይደለምን ፡
ለምን ፡ አትፈሩ ።
፲፩ በባሕርና ፡ በየብስ ፡ ለሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡
ጥበብንና ፡ ትምህርትን ፡ የሰጠ ፡ ማነው ፡ በመ
ርከብ ፡ ተጭነው ፡ የሚሄዱ ፡ እነዚያ ፡ ነጋድያን ፡
ባሕርን ፡ የሚፈሩ ፡ አይደለምን ፡ ኃጥአን ፡ ግን ፡
እግዚአብሔርን ፡ አይፈሩትም ።
፲፪ በነዚያም ፡ ወራቶች ፡ ጭንቅ ፡ መከራ ፡ በናንተ ፡
ቢያመጣባችሁ ወዴት ፡ ትሸሻላችሁ ፡ ከየትስ ፡
ትድናላችሁ ።
፲፫ የተናገረውንም ፡ ነገር ፡ በናንተ ፡ ቢያመጣባ
ችሁ ፡ የምትፈሩ ፡ የምትደነግጡ ፡ አይደለምን ፡
ብርሃኖችስ ፡ ሁሉ ፡ በጽኑ ፡ ፍራት ፡ ተይዘው ፡
የሚፈሩ ፡ የሚደነግጡ ፡ አይደለምን ።
፲፬ ምድርስ ፡ ሁሉ ፡ በጽኑ ፡ ፍራት ፡ ተይዛ ፡ የምት
ንቀጠቀጥ ፡ ለኀልፈትስ ፡ የምትቸኵል ፡ አይደ
ለምን ።
፲፭ መላእክትም ፡ ሁሉ ፡ የተያዙትን ፡ ይጨርሳሉ ፡
ከክብር ፡ ባለቤት ፡ ከእግዚአብሔርም ፡ ፊት ፡
ሊሠወሩ ፡ ይወዳሉ ።
፲፮ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ያሉ ፡ ሰዎችም ፡ ይርዳሉ ፡ ይተ
ዋወካሉ ፡ እናንተ ፡ ኃጥአን ፡ ግን ፡ ለዘላለሙ ፡
የተረገማችሁ ፡ ናችሁ ፡ ፍቅር ፡ አንድነትም ፡
የላችሁም ።
፲፯ እናንተ ፡ የጻድቃን ፡ ሰውነቶች ፡ አትፍሩ ፡ በው
ነት ፡ ነገርም ፡ የሞታችሁ ፡ ሰዎች ፡ ዋጋች
ሁን ፡ እንድታገኙ ፡ ተስፋ ፡ አድርጉ ።
፲፰ ሰውነታችሁ ፡ በጽኑ ፡ መከራ ፡ በልቅሶ ፡ በት
ልቅ ፡ መከራ ፡ ተይዛ ፡ በኀዘን ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡
ወርዳለችና ፡ አትዘኑ ።
፲፱ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ውሾ ፡ ውሾ ፡ በተባላችሁበት ፡
ቀን ፡ ጽኑ ፡ መከራና ፡ ስድብንም ፡ በተቀበላችሁ
በት ፡ ቀን ፡ ሞታችሁ ፡ እንጂ ፡ እንደ ፡ በኀነታ
ችሁ ፡ መጠን ፡ በሕይወተ ፡ ሥጋ ፡ ባላችሁ ፡
ሰውነታችሁ ፡ ተድላ ፡ ደስታን ፡ አላገኘምና ፡
አትዘኑ ።
በሞታችሁም ፡ ጊዜ ፡ ኃጥአን ፡ ጻድቃን ፡ እኛ ፡ ፳
እንደሞትን ፡ ሞቱ ፡ በሥራቸውስ ፡ ጥቅማቸው ፡
ምንድነው ፡ ይላሉ ።
በመከራና ፡ በኀዘን ፡ ሳሉ ፡ እነሆ ፡ እንደኛ ፡ ፳፩
ሞቱ ፡ ከኛ ፡ ብልጫቸው ፡ ምንድነው ፡ ከዛሬ ፡
ጀምሮ ፡ በሞት ፡ ተካከልን ፡ ምንን ፡ ያገኛሉ ፡
እነሱ ፡ እንደኛ ፡ እነሆ ፡ ሙተዋልና ፡ ከዛሬም ፡
ጀምሮ ፡ ለዘላለሙም ፡ ብርሃንን ፡ አያውምና ፡
ለዘላለሙ ፡ ምን ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ያያሉ ።
እናንተ ፡ ኃጥአን ፡ መብል ፡ መጠጥ ፡ ኃጢአትና ፡ ፳፪
ቅሚያ ፡ ገንዘብ ፡ ማጠራቀምና ፡ ሰውን ፡ መግ
ፈፍ ፡ በማረ ፡ ዘመንም ፡ ተድላ ፡ ደስታውን ፡
ማየት ፡ በቃችሁ ፡ እላችኋለሁ ።
ሞተው ፡ እስኪጠፉ ፡ ድረስ ፡ ግፉ ፡ ሁሉ ፡ በነሱ ፡ ፳፫
ላይ ፡ አልተገኘምና ፡ መጨረሻቸው ፡ ፍቅር ፡
አንድነት ፡ እንደሆነ ፡ ጻድቃንን ፡ አያችኋቸ
ውን ።
ተፈጥረውም ፡ እንዳልተፈጠሩ ፡ የሆኑ ፡ ሰውነ ፡ ፳፬
ቶታቸውም ፡ በመከራ ፡ ተይዘው ፡ ወደ ፡ መቃ
ብር ፡ ወረዱ ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

በክብሩና ፡ በገናና ፡ ጌትነቱ ፡ በገናንነቱና ፡ ፩
በከበረ ፡ መንግሥቱም ፡ ጻድቃን ፡ ለናንተ ፡
ዛሬ ፡ እነግራችኋለሁ ።
ይህንንም ፡ ምሥጢር ፡ እኔ ፡ አውቄአለሁና ፡ ፪
በሰማይ ፡ ሰሌዳነትም ፡ ያለውን ፡ አንብቤአለ
ሁና ፡ ቅዱሳን ፡ የጻፉትንም ፡ አይቻለሁና ፡
እነግራችኋለሁ ።
በጎው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ተድላ ፡ ደስታውም ፡ ክብ ፫
ሩም ፡ ተዘጋጅቶላቸዋልና ፡ የነሱ ፡ ነገር ፡ በው
ስጣቸው ፡ ፈጽሞ ፡ ተጽፎላቸው ፡ አገኘሁ ።
በቀናና ፡ በውነት ፡ ነገር ፡ በብዙም ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ ፬
ለሞቱ ፡ ሰዎች ፡ ሰውነት ፡ ተጻፈላቸው ፡ የድካ
ማችሁም ፡ ዋጋ ፡ ይሰጣችኋል ፡ የናንተም ፡ እድ
ላችሁም ፡ ከልሞቱ ፡ ሰዎች ፡ እድል ፡ ይበልጣል ።
በሃይማኖት ፡ የሞታችሁ ፡ የናንተ ፡ ሰውነት ፡ ፭
አርፋ ፡ ትኖራለች ፡ ሰውነቶቻቸውም ፡ ፈጽ
መው ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ።
መታሰቢያቸውም ፡ በገናና ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፮
ፊት ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ዘመን ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፡
አሁንም ፡ መከራቸውን ፡ አትፍሩት ።
የሞታችሁ ፡ ኃጥአን ፡ በኃጢአታችሁ ፡ በሞታ ፯
ችሁ ፡ ጊዜ ፡ ወዮላችሁ ።
እንደናንተ ፡ ያሉ ፡ ኃጥአንም ፡ ስለናንተ ፡ ኃጥ ፰
አን ፡ እናንተ ፡ ንዑዳን ፡ ክቡራን ፡ ናችሁ ፡ ባለ ፡
ዘመናቸውም ፡ ሁሉ ፡ ተድላ ፡ ደስታውን ፡ አዩ ።
ዛሬም ፡ በባለጠግነትና ፡ በተድላ ፡ በደስታ ፡ ሳሉ ፡ ፱
ሞቱ ፡ ሰልፉንና ፡ መከራውንም ፡ በሕይወተ ፡
ሥጋ ፡ ሳሉ ፡ አላዩም ፡ በጌትነትም ፡ ሳሉ ፡ ሞቱ ፡
በሕይወተ ፡ ሥጋም ፡ ሳሉም ፡ መቻያም ፡ አል

ተደረገባቸውም ።
፲፡ ነፍሶቻቸውን፡መላእክት፡ወደ፡ሲኦል፡እንዲ
ያወርዷቸው፡ጽኑ፡መከራቸውስ፡ክፉ፡ነገሮ
ችን ፡ እንዲሆኑባቸው ፡ አታውቋቸውምን ።
፲፩፡ ሰውነታችሁ፡በጽኑ፡መከራና፡በጨለማ፡በሚ
ነድ ፡ በሚያላልብ ፡ መከራም ፡ ወደ ፡ ጽኑ ፡
መቃያ ፡ ትገባለች ፡ ጽኑ ፡ መቃያም ፡ ለልጅ ፡
ልጅ ፡ ዘመን ፡ ትደረጋለች ።
፲፪፡ ፍቅር ፡ አንድነት ፡ የላችሁምና ፡ ወዮላችሁ ፡
በሕይወተ ፡ ነፍስ ፡ ያሉ ፡ ደናግልና ፡ ለሕጋው
ያን ፡ በደከምንበት ፡ ወራት ፡ ለናንተ ፡ ድከምን፡
ደከምን ፡ አትበሏቸው ።
፲፫፡ መከራውን ፡ ሁሉ ፡ አየን ፡ ብዙ ፡ መከራዎች
ንም ፡ ተቀበልን ፡ ጨርሰን ፡ ጠፋን፡ከዚያ፡አስ
ቀድሞም ፡ አነስን ፡ ሰውነታችንም ፡ አነሰች ፡
በዚሁም ፡ ጠፋን ።
፲፬፡ በነገር ፡ የሚረዳን ፡ የለም ፡ በነሱ ፡ ሥራ ፡ ደከ
ምን ፡ በነሱ ፡ ሥራ ፡ ስንደክም ፡ ምንምን ፡
ተስፋ፡ አላገኘንም፡ በመከራውም ፡ ተጨንቀን፡
ጠፋን ፡ አትበሏቸው ።
፲፭፡ ከዛሬ ፡ ነገ ፡ ድኅነትን ፡ እናያ ፡ ዘንድ ፡ ተስፋ ፡
አደረግን ፡ ገዥ ፡ ልንሆን ፡ ተስፋ ፡ አደረግን ፡
ተገዥ ፡ ሆን ፡ ሥራውን ፡ ስንሠራ ፡ ደከምን ።
፲፮፡ በደከምንበትም ፡ ድካም ፡ ላይ ፡ ግዳጃችንን ፡
አልጨረስንም ፡ ለኃጥአንም ፡ መብሎችን ፡ ሆን፡
በደለኞች ፡ ሰዎችም ፡ አገዛዛቸውን ፡ አጸኑብን ።
፲፯፡ እኛን ፡ የሚጠሉን ፡ እኛንም ፡ የሚወጉን ፡
ሰዎች ፡ በኛ ፡ ሠለጠኑብን ፡ ለሚጠሉንም ለጠ
ላቶቻችን ፡ አንገታችን ፡ ዝቅ ፡ ዝቅ ፡ አደረግን ፡
እነሱ ፡ ግን ፡ አልራሩልንም ።
፲፰፡ ከነሱ ፡ ሸሽተን ፡ ከመከራው ፡ ልናርፍ ፡ ወደ
ድን ፡ ከነሱም ፡ ሸሽተን ፡ የምንድንበት ፡ ቦታ ፡
አላገኘንም ።
፲፱፡ በመከራውም ፡ ተይዘን ፡ በመላእክት ፡ ዘንድ ፡
ጠላቶቻችንን ፡ ከሠሥናቸው ፡ በሚጠሉን ፡ ጠላ
ቶቻችንም ፡ ላይ ፡ ጮህን ፡ ጩኸታችንን ፡
ግን ፡ አልሰሙንም ፡ ቃላችንንም ፡ ሊሰሙን ፡
አይወዱም ።
፳፡ ለሚቀሙን ፡ ገንዘባችንንም ፡ የሚበሉብን ፡
ያሳነሱንን ጠላቶቻችንን ፡ ይረዷቸዋል ፡ ግፉ
ቸውንም ፡ ይሠውሩላቸዋል ፡ እንጂ ፡ ገንዘባች
ንን ፡ የሚበሉብን ፡ ሰዎች ፡ አገዛዛቸውን ፡ ከኛ ፡
አያጠፉልንም ።
፳፩፡ በየሀገሩ ፡ ይበትኑናል ፡ ይገሉናል ፡ ሞታቸው
ንም ፡ ይሠውሩብናል ፡ እንጂ ፡ እጃቸውን ፡ እን
ዲያነሡ ፡ አላሰቡም ፡ አትበሏቸው ።
፳፪፡ ጻድቃን ፡ የእናንተን ፡ ነገር ፡ በገናና ፡ ፈጣሪ ፡
በጌትነቱ ፡ ፊት ፡ ለበጎ ፡ ነገር ፡ መላእክት ፡ በሰ
ማዩ ፡ እንዲያስቡት ፡ እነግራችኋለሁ ።
፳፫፡ በገናና ፡ ፈጣሪ ፡ ጌትነቱ ፡ ፊት ፡ ስማችሁ ፡ ይጻ
ፋል ፡ በቀድሞው ፡ ዘመን ፡ በክፉ ፡ ነገር ፡ በደ
ከሙም ፡ ሁሉ ፡ ጕስቁላችኋልና ፡ ዋጋችሁን ፡
እንድታገኙ ፡ ተስፋ ፡ አድርጉ ።
፳፬፡ አሁንም ፡ እንደ ፡ ሰማይ ፡ ብርሃን ፡ አብርታችሁ ፡
ትታያላችሁ ፡ የሰማይም ፡ ደጃፍ ፡ ይከፈትላች
ኋል ።
፳፭፡ ምስጋናችሁንም ፡ በሚገባ ፡ አመስግኑ ፡ መላእ
ክት ፡ መከራችሁን ፡ ሁሉ ፡ ገንዘባችሁን ፡ የሚ
ቀሟቸውን ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ይመራሉና ፡ ተድ
ላችሁ ፡ ደስታችሁ ፡ ይገለጣል ።
፳፮፡ እንደ ፡ መላእክት ፡ በሰማይ ፡ ታደርጉት ፡ ዘንድ ፡
ያላችሁ ፡ ብዙ ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ እንድታደርጉ ፡
ተስፋ ፡ አድርጉ ፡ አለኝታችሁንም ፡ አትተው ፡
ጽኑ ፡ ፍርድ ፡ በሚደረግበት ፡ ቀን ፡ ትሠወሩ ፡
ዘንድ ፡ ይላችሁ ፡ አይደለም ።
፳፯፡ እንደ ፡ ኃጥአንም ፡ ሁናችሁ ፡ አትገኙ ፡ ከናን
ተም ፡ የተነሣ ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡
የዘላለም ፡ መቃያ ፡ ትደረጋለች ።
፳፰፡ አሁንም ፡ ጻድቃን ፡ ኃጥአንን ፡ ጸንተው ፡ በፈ
ቃዳቸው ፡ ተዘጋጅተው ፡ በያችኋቸው ፡ ጊዜ ፡
አትፍሩ ።
፳፱፡ ከሰማይ ፡ መላእክት ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ትሆኑ ፡
ዘንድ ፡ አላችሁና ፡ እነሱ ፡ ከሚሠሩት ፡ ግፍ ፡
እራቁ ፡ እንጂ ፡ ከነሱ ፡ ጋራ ፡ የተባበራችሁን ፡
አትሁኑ ።
፴፡ እናንተ ፡ ኃጥአን ፡ መላእክት ፡ አይመረምሩ
ንም ፡ ኃጢአታችንም ፡ ሁሉ ፡ አይጻፍብንም ፡
ትላላችሁና ፡ በየቀኑ ፡ የሠራችሁትንና ፡ ኃጢ
አታችሁን ፡ ሁሉ ፡ ይጽፉ ፡ ዘንድ ፡ አላቸው ።
፴፩፡ ጨለማና ፡ ብርሃን ፡ ሌትና ፡ ቀን ፡ ኃጢአታ
ችሁን ፡ ሁሉ ፡ እንዲገልጡባችሁ ፡ አሁንም ፡
እኔ ፡ ገልጬ ፡ እነግራችኋለሁ ፡ ይህንንም ፡
በልቡናችሁ ፡ አትዘንጉ ፡ ሐሰትም ፡ አታድርጉ ።
፴፪፡ የቀናውን ፡ ነገር ፡ ወደ ፡ ጥመት ፡ አትመልሱት ፡
የገነነ ፡ የከበረ ፡ የእግዚአብሔርንም ፡ ነገር ፡
ሐሰት ፡ አታድርጉት ፡ ለጽኑ ፡ ኃጢአት ፡ ነው ፡
እንጂ ፡ ሐሰታችሁም ፡ ሁሉ ፡ ዝንጋታችሁም ፡
ሁሉ ፡ እውነት ፡ አይደለችምና ፡ ጣዖታችሁን ፡
አታመስግኑት ።
፴፫፡ ብዙዎች ፡ ኃጥአን ፡ የቀናውን ፡ ነገር ፡ ወደ ፡
ጥመት ፡ ፈጽመው ፡ እንዲመልሱት ፡ ዛሬም ፡
እኔ ፡ ይህንን ፡ ምሥጢር ፡ መርምሬ ፡ አውቀዋ
ለሁ ።
፴፬፡ ክፉዎችንም ፡ ነገሮችን ፡ ይናገራሉ ፡ ጽኑ ፡ ጽኑ ፡
ነገሮችንም ፡ ልብ ፡ ወለድ ፡ በሐሰት ፡ ይናገ
ራሉ ፡ በነገራቸውም ፡ ላይ ፡ የሐሰት ፡ መጻሮ
ችን ፡ ይጽፋሉ ።
፴፭፡ ነገር ፡ ግን ፡ ነገሮቼን ፡ ሁሉ ፡ በቀና ፡ ነገር ፡ በንደ
በቶቻቸው ፡ ሊጽፉ ፡ ላይለውጡ ፡ አስቀድሚ ፡
ስለነሳቸው ፡ ያዳነሁባቸውን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡
በቀና ፡ ነገር ፡ ይጽፉት ፡ ዘንድ ፡ እንጂ ፡ ነገሮቼ
ንም ፡ ባያሳንሱ ፡ በተገባ ፡ ነበር ።
፴፮፡ ለደጋግ ፡ ሰዎች ፡ ላዋቆችም ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡
ብዙ ፡ ጥበብና ፡ የቀና ፡ ነገርም ፡ ሊሆኗቸው ፡
መጻሕፍት ፡ ይሰጧቸዋልና ፡ ለኃጥአንም ፡ ይገለ
ጡላቸዋልና ፡ ሌላ ፡ ምሥጢርንም ፡ አውቃለሁ ።
፴፯፡ እነሱ ፡ ያምኑባቸዋል ፡ በነሱም ፡ ደስ ፡ ይላቸ
ዋል ፡ ከነሱ ፡ ይልቅ ፡ የቀና ፡ ነገር ፡ ያለባቸው ፡

ሕጎችን ፡ ሁሉ ፡ ያወቁ ፡ ጻድቃንም ፡ ሁሉ ፡
ዋጋቸውን ፡ ያገኛሉ ።
፴፰ በነዚያም ፡ ወራቶች ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ላሉ ፡
ሰዎች ፡ ጥበባቸውን ፡ ያስተምሩዋቸው ፡ ዘንድ ፡
ጌታ ፡ አሰሟቸው ፡ አለ ።
፴፱ እናንተ ፡ መምሮቻቸው ፡ ናችሁና ፡ የመምርነ
ታችሁንም ፡ ዋጋ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ታገኛላች
ሁና ፡ አስተምሯቸው ፡ አለ ።
፵ በሕይወተ ፡ ሥጋ ፡ ሳሉ ፡ በቀና ፡ ሥራዎች ፡
ልጆችና ፡ እኔ ፡ ከነሱ ፡ ጋር ፡ ለዘላለሙ ፡ አንድ ፡
እንሆናለንና ፡ አስተምሯቸው ፡ ፍቅር ፡ አንድ
ነትም ፡ ይደረግላችኋልና ፡ በውነት ፡ የቀና ፡
ሕጉንም ፡ የምትጠብቁ ፡ ሰዎች ፡ ደስ ፡ ይበላ
ችሁ ፡ አለ ።

## ምዕራፍ ፡ ፵፩ ።

፩ ከብዙ ፡ ቀንም ፡ በኋላ ፡ ልጁ ፡ ማቱሳላ ፡ ልጁ ፡
ላሜህን ፡ ሚስት ፡ አጋባው ፡ ከሱም ፡ ፀንሳ ፡
ወንድ ፡ ልጅ ፡ ወለደች ።
፪ ሰውነቱም ፡ እንደ ፡ ዕንቍ ፡ ነጭ ፡ ሆነ ፡ እንደ ፡
ጽጌ ፡ ረዳም ፡ ቀይ ፡ ነው ፡ የራሱም ፡ ጠጕር ፡
እንደ ፡ ነጭ ፡ ብዝት ፡ ነው ፡ የተሸራሸ ፡ ነው ፡
ዓይኖቹም ፡ ያማሩ ፡ ናቸው ።
፫ ዓይኖቹንም ፡ በገለጠ ፡ ጊዜ ፡ ቤቱን ፡ ሁሉ ፡
እንደ ፡ ፀሐይ ፡ አበራ ፡ ቤቱም ፡ ሁሉ ፡ ፈጽሞ ፡
በራ ፡ ከዋላጂቱም ፡ እጅ ፡ በተነሣ ፡ ጊዜ ፡ ነገር ፡
ጀመረ ፡ የቸርነት ፡ ጌታ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ምስ
ጋናን ፡ ተናገረ ።
፬ ከሱም ፡ የተነሣ ፡ አበቱ ፡ ላሜህ ፡ ፈርቶ ፡ ሸሸ ፡
ወዳበቱ ፡ ወደ ፡ ማቱሳላም ፡ መጣ ፡ እኔ ፡ ልውጥ ፡
ልጅ ፡ ወለድሁ ፡ እንደ ፡ ሰውም ፡ አይደለም ።
፭ የሰማይ ፡ መላእክት ፡ ልጆቹንም ፡ ይመስላል ፡
ፍጥረቱም ፡ ልዩ ፡ ናት ፡ እንደኛም ፡ አይደለም ፡
ዓይኖቹም ፡ እንደ ፡ ፀሐይ ፡ እግሮች ፡ ናቸው ፡
ፊቱም ፡ የበራ ፡ ነው ፡ አለ ።
፮ ከመላእክት ፡ የተወለደ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ከኔስ ፡
ያልተወለደ ፡ ይመስለኛል ፡ እኔስ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡
በሱ ፡ ዘመን ፡ ድንቅ ፡ ሥራ ፡ እንዳይሠራ ፡ ብዬ ፡
እፈራለሁ ።
፯ መኖሪያው ፡ ከመላእክት ፡ ጋራ ፡ ነውና ፡ ወዳበ
ታችን ፡ ወደ ፡ ሄኖክ ፡ ትሔድ ፡ ዘንድ ፡ ከሱም ፡
እውነቱን ፡ ነገር ፡ ትሰማ ፡ ዘንድ ፡ አሁንም ፡
አባቴ ፡ ፈጽሜ ፡ እለምንሀ ፡ ዘንድ ፡ አለሁ ፡
፰ ማቱሳላም ፡ የልጁን ፡ ነገር ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡
በዚያ ፡ እንዳለሁ ፡ ሰምቷልና ፡ ጮኸ ፡ እኔም ፡
ቃሉን ፡ ሰማሁት ፡ አለ ።
፱ ወደሱም ፡ መጣሁ ፡ ወደኔ ፡ መጥተሃልና ፡ ልጄ ፡
እነሆ ፡ አለሁ ፡ አልኩት ።
፲ ስለ ፡ ታላቁ ፡ ነገር ፡ ስለ ፡ ቀረብሁበት ፡ ስለ ፡
ጭንቅ ፡ ራእይም ፡ ወዳንተ ፡ መጣሁ ፡ ብሎ ፡
መለሰልኝ ።
፲፩ መልኩ ፡ ፍጥረቱም ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ፍጥረት ፡
ያልሆነ ፡ መልኩም ፡ ከዕንቍ ፡ ይልቅ ፡ የሚነጣ ፡
ከጽጌ ፡ ረዳም ፡ የሚቀላ ፡ የራሱም ፡ ጠጕር ፡
ከብዝት ፡ ይልቅ ፡ የሚነጣ ፡ ዓይኖቹም ፡ እንደ ፡
ፀሐይ ፡ እግር ፡ የሚያበሩ ፡ ልጅ ፡ ለልጄ ፡ ለላ
ሜህ ፡ ተወልዷልና ፡ አባቴ ፡ አሁንም ፡ ስማኝ ።
ዓይኖቹንም ፡ በገለጠ ፡ ጊዜ ፡ ቤቱን ፡ ሁሉ ፡ አበራ ፡ ፲፪
ከዋላጅቱም ፡ እጅ ፡ ተነሥቶ ፡ አፉንም ፡ ከፍቶ ፡
የሰማይ ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰገነው ።
አባቱ ፡ ልጄ ፡ ላሜህም ፡ ፈርቶ ፡ ወደኔ ፡ ሸሸ ፡ ፲፫
ከሰማይ ፡ መላእክት ፡ የተወለደ ፡ አስመሰለው ፡
እንጂ ፡ እሱ ፡ ከሱ ፡ እንደተወለደ ፡ አላመነም ።
እውነቱን ፡ ትነግረኝ ፡ ዘንድ ፡ እነሆ ፡ እኔ ፡ ወዳ ፲፬
ንተ ፡ መጣሁ ።
እኔም ፡ ሄኖክ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንግዳ ፡ ነገር ፡ ፲፭
ይሠራል ፡ ብዬ ፡ የሱን ፡ ነገር ፡ ተናገርሁ ፡ ያባቴ ፡
የያሬድ ፡ የልጁ ፡ ወገኖች ፡ ከሰማይ ፡ በላይ ፡
ያለ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕጉን ፡ አፍርሰዋልና ፡
ይህንን ፡ በራዕይ ፡ ፈጽሜ ፡ አይቼ ፡ ነገርሁህ ፡
አለው ።
እነሆ ፡ ኃጢአትንም ፡ ይሠራሉ ፡ ሥራቱንም ፡ ፲፮
ያፈርሳሉ ፡ ከሴቶችም ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ሆኑ ፡
ከነሱም ፡ ጋር ፡ ኃጢአትን ፡ ይሠራሉ ፡ ከነሱም ፡
ሚስቶችን ፡ አግብተው ፡ ከነሱ ፡ ልጆችን ፡
ወለዱ ፡ በዚህም ፡ ዓለም ፡ ሁሉ ፡ ጽኑ ፡ ጥፋት ፡
ይደረጋል ።
ጥፋት ፡ ያለበት ፡ ውሀ ፡ ይወርዳል ፡ ታላቁም ፡ ፲፯
ጥፋት ፡ በንዱ ፡ ዓመት ፡ ይደረጋል ፡ ለናንተ ፡
የተወለደ ፡ ልጅ ፡ ይኸ ፡ ነው ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡
እሱ ፡ ብቻ ፡ ይቀራል ፡ ሦስቱም ፡ ልጆቹ ፡ ከሱ ፡
ጋራ ፡ ከማየ ፡ አይህ ፡ ይድናሉ ።
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ያለው ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በሞተ ፡ ፲፰
ጊዜ ፡ እሱ ፡ ይድናል ፡ ልጆቹም ፡ አርበኞች ፡
ሰዎችን ፡ ይወልዳሉ ፡ እነዚህም ፡ ሥጋውያን ፡
ናቸው ፡ እንጂ ፡ መንፈሳውያን ፡ አይደሉም ።
ጽኑ ፡ መቅሠፍትም ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ይደረጋል ፡ ፲፱
ምድርም ፡ ከኃጢአት ፡ ሁሉ ፡ ትነጻለች ።
አሁንም ፡ ይህ ፡ የተወለደ ፡ ልጅ ፡ በእውነት ፡ ፳
የሱ ፡ ልጅ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ለልጅህ ፡ ለላሜህ ፡
ንገረው ፡ እሱ ፡ ከጥፋት ፡ የቀረ ፡ ይሆንላችኋ
ልና ፡ ስሙንም ፡ ኖኅ ፡ ብለህ ፡ ጥራው ፡ በሱ ፡
ዘመን ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ትጨረስ ፡ ዘንድ ፡ ካላት ፡
በደል ፡ ሁሉና ፡ ከኃጢአትም ፡ ሁሉ ፡ የተነሣ ፡
ወደዚህ ፡ ዓለም ፡ ከምትመጣ ፡ ጥፋት ፡ ልጆ
ቹና ፡ እሱ ፡ ይድናሉ ፡ መላእክት ፡ ያወቋቸውን ፡
ምሥጢሮች ፡ አውቃለሁና ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡
በዚህ ፡ ዓለም ፡ አስቀድማ ፡ ከተጨረሰችው ፡
ኃጢአት ፡ ይልቅ ፡ ፈጽማ ፡ የምትበልጥ ፡ ግፍ ፡
ትደረጋለች ፡ እሱ ፡ እግዚአብሔር ፡ ገልጦልኛ
ልና ፡ ነግሮኛልና ፡ በሰማይ ፡ ሰሌዳነት ፡ የተጻፈ
ውን ፡ አወቅሁ ፡ አነበብሁ ።
ሕጉን ፡ የምትጠብቅ ፡ ልጅ ፡ (አብርሃም ፡ ) እስክ ፳፩
ትነሣ ፡ ድረስ ፡ አንዲቱ ፡ ልጅ ፡ ካንዲቱ ፡ ልጅ ፡
ይልቅ ፡ አብልጣ ፡ ትበድላለችና ፡ በነሱ ፡ የተጻ
ፈውን ፡ አየሁ ፡ በደል ፡ ትጠፋለች ፡ ኃጢአ
ትም ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ከሰው ፡ ትርቃለች ፡ በጎ
ውም ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በሷ ፡ ይመጣል ፡ ይህ ፡ የተ

ወለደ ፡ ልጅ ፡ በውነት ፡ የሱ ፡ ልጅ ፡ ነውና ፡
ሐሰትም ፡ አይደለምና ፡ አሁንም ፡ ልጄ ፡ ሂደህ ፡
ለልጅህ ፡ ለላሜህ ፡ ንገረው ፡ ማቱሳላም ፡ ያባቱ ፡
የሄኖክን ፡ ነገር ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ሥራውን ፡ ሁሉ ፡
በስውር ፡ ገልጦለታልና ፡ ነገሩን ፡ ሰምቶ ፡ ተመ
ለሰ ።
፳፪ ፡ ከጥፋቷ ፡ ሁሉ ፡ አድኖ ፡ ምድርን ፡ ደስ ፡ ያሰኛ
ታልና ፡ የዚያን ፡ የልጅ ፡ ስሙን ፡ ኖኅ ፡ አለው ።

ምዕራፍ ፡ ፴፪ ።

፩ ፡ ለልጁ ፡ ለማቱሳላ ፡ ከሱም ፡ በኋላ ፡ ለሚ
መጡ ፡ ሰዎች ፡ በኋላ ፡ ዘመንም ፡ ሥራቱን ፡
ለሚጠብቁ ፡ ሰዎች ፡ ሄኖክ ፡ የጻፈው ፡ ሁለተኛ ፡
መጽሐፍ ፡ ይህ ፡ ነው ።
፪ ፡ ክፉውን ፡ ሥራ ፡ የሚሠሩ ፡ ሰዎች ፡ እስቲጨ
ረሱ ፡ ድረስ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የበደሉ ፡ ሰዎ
ችም ፡ ሠራዊት ፡ እስቲጨረስ ፡ ይህንን ፡ የሠራ
ችሁ ፡ እናንተ ፡ በነዚህ ፡ ወራቶች ፡ ትቆያላችሁ ።
፫ ፡ ስማቸው ፡ ከጻድቃን ፡ ቍጥር ፡ ይፋቅ ፡ ዘንድ ፡
አለውና ፡ ልጃቸውም ፡ ለዘላለሙ ፡ ይጠፋልና ፡
እናንተ ፡ ግን ፡ በኃጢአት ፡ የመጣው ፡ መከራ ፡
እስቲያልፍ ፡ ድረስ ፡ ደጅ ፡ ጥኑ ፡ ልጆቻቸውም ፡
ይሞታሉ ፡ በማይታይም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ቦታ ፡
ሁነው ፡ ጬኸው ፡ ያለቅሳሉ ፡ በዚያም ፡ ቦታ ፡
ምድር ፡ የለምና ፡ በገሃነም ፡ ይቃጠላሉ ። ከጥ
ልቅነቱ ፡ የተነሣ ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ማየትን ፡ አልቻ
ልሁምና ፡ በዚያ ፡ ቦታ ፡ እንደማይታይ ፡ ደመና ፡
ያለ ፡ አየሁ ።
፬ ፡ የእሳቱንም ፡ ጥዕይ ፡ ሲነድ ፡ አየሁት ፡ ይኸውም ፡
የሚያስፈራ ፡ ነው ፡ እንደሚያስፈሩ ፡ ተራሮ
ችም ፡ በእሳት ፡ ተከበዋል ፡ ወዲያ ፡ ወዲህ ፡
እያሉ ፡ ይተዋወካሉ ።
፭ ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ካሉ ፡ ከሰባቱ ፡ ሊቃነ ፡ መላእክት ፡
አንዱን ፡ መልአክ ፡ ብቻውን ፡ የሚነድ ፡ የእሳት ፡
ጥዕይ ፡ የልቅሶም ፡ ቃል ፡ የፍጻም ፡ ጬኸት ፡
የጽኑ ፡ መከራ ፡ ቃል ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ሰማይ ፡ አይ
ደለምና ፡ ይህ ፡ የሚያስፈራ ፡ ቦታ ፡ ምንድነው ፡
ብዬ ፡ ጠየቅሁት ።
፮ ፡ ይህ ፡ የምታየው ፡ ቦታ ፡ የተነቀፉ ፡ ሰዎችና ፡
የኃጥአን ፡ ልጆች ፡ ኃጢአትንም ፡ የሚሠሩ ፡
ሰዎች ።
፯ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ይሠሩ ፡ ዘንድ ፡ ያላቸው ፡ በነቢ
ያት ፡ አንደበት ፡ እግዚአብሔር ፡ ያናገረውን ፡
ነገር ፡ ሁሉ ፡ ወዳለመሆን ፡ የሚመልሱ ፡ ሰዎ
ችም ፡ በዚያ ፡ ይወድቃሉ ፡ አለኝ ።
፰ ፡ መላእክት ፡ ያነቢቻቸው ፡ ዘንድ ፡ ለተዋረዱ ፡ ልጆ
ችና ፡ ለኃጥአን ፡ ይደርስባቸው ፡ ዘንድ ፡ ያለው
ንም ፡ ያውቁ ፡ ዘንድ ፡ ከነሳቸው ፡ ወገን ፡ በሰ
ማይ ፡ የተጻፉ ፡ አሉና ፡ በዚያ ፡ ይወድቃሉ ፡
አለኝ ።
ሥጋቸውን ፡ መከራ ፡ ያስቻሉ ፡ በፈጣሪያቸ ፱ ፡
ውም ፡ አምነው ፡ መከራ ፡ የተቀበሉ ፡ በክፉ ፡
ሰዎችም ፡ የተነሣ ፡ የገሰቈሉ ፡ ፈጣሪያቸው
ንም ፡ የወደዱ ፡ ሰዎች ፡ ብርና ፡ ወርቅን ፡ አይ
ወዱም ። ሥጋቸውን ፡ ለመከራ ፡ የሰጡ ፡ ራሳቸ
ውን ፡ እንደ ፡ ሞተች ፡ ሰውነት ፡ አደረጉ ፡ እንጂ ፡
ከተፈጠሩ ፡ጀምሮ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ያሉ ፡ መብ
ሎችንም ፡ ያልወደዱ ፡ ሰዎች ፡ የዚህን ፡ ዓለም ፡
ሹመት ፡ ሽልማት ፡ አልወደዱም ። ይህንንም ፡
አስተዋሉ ፡ ጌታም ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ስሙን ፡ ያመ
ሰግኑ ፡ ዘንድ ፡ ፈተናቸው ፡ ሰውነቶቻቸውም ፡
በንጽሕና ፡ ተገኙ ።
የቀረውንም ፡ ሥጋቸውን ፡ ሁሉ ፡ በመጻፎች ፡ ፲ ፡
ተናገርኩ ፡ እሊህ ፡ ከሕፃንነታቸው ፡ ጀምሮ ፡
ዘለዓለም ፡ ጸንቶ ፡ የሚኖር ፡ ሰማያዊ ፡ ሕጉን ፡
ሲወዱት ።
ለክፉፉ ፡ ሰዎችም ፡ መከራ ፡ ሲቀበሉ ፡ ከነሳቸ ፲፩ ፡
ውም ፡ ተግዳሮትን ፡ ስድብንም ፡ ሲሰሙ ፡ እኔ
ንም ፡ ሊያመሰግኑኝ ፡ ገስቍለዋልና ፡ ለየራሳ
ቸው ፡ ዋጋቸውን ፡ ስጣቸው ።
አሁንም ፡ እውቀት ፡ ካላቸው ፡ ሰዎች ፡ የተወ ፲፪ ፡
ለዱ ፡ ደጎች ፡ የሆኑ ፡ ሰዎች ፡ ነፍሳቸውን ፡ እጠ
ራለሁ ፡ ለሃይማኖታቸው ፡ እንደሚገባቸው ፡
መጠን ፡ በሥጋቸው ፡ ክብርን ፡ ያላገኙ ፡ በመ
ከራ ፡ ከክርስቶስ ፡ ለተወለዱ ፡ ለጻድቃን ፡ መከ
ራቸውን ፡ እለውጥላቸዋለሁ ።
የከበረ ፡ ስሙን ፡ የወደዱትን ፡ ሰዎችንም ፡ በበራ ፡ ፲፫ ፡
ብርሃን ፡ ከገሃነም ፡ አወጣቸዋለሁ ። አንዱንም ፡
አንዱንም ፡ በከበረ ፡ በክብር ፡ ዙፋን ፡ አኖረ
ዋለሁ ፡ የፈጣሪ ፡ ፍርዱ ፡ እውነት ፡ ነውና ፡
ቍጥር ፡ በሌላቸው ፡ ዘመኖችም ፡ ያበራሉ ።
በቀኑ ፡ ሥራዎች ፡ በሚገኝ ፡ በመንግሥተ ፡ ፲፬ ፡
ሰማይ ፡ ለታመኑ ፡ ሰዎች ፡ የሃይማኖታቸውን ፡
ዋጋ ፡ ይሰጣቸዋልና ።
በብርሃን ፡ ሲያበሩ ፡ ሲያመሰግኑም ፡ ጻድቃን ፡ ፲፭ ፡
በድንቁርና ፡ ከዲያብሎስ ፡ የተወለዱ ፡ ኃጥአ
ንን ፡ በገሃነም ፡ ሲወድቁ ፡ ያዩዋቸዋል ፡ ኃጥአ
ንም ፡ ጻድቃንን ፡ በመንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ሲያ
በሩ ፡ ያዩዋቸዋል ።
እነሱም ፡ በተጻፈላቸው ፡ ዘመኖችና ፡ ቀኖች ፡ ፲፮ ፡
ጸንተው ፡ ይኖራሉ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ለዘለዓ
ለሙ ፡ በውነት ፡ ክብር ፡ ምስጋና ፡ ይግባውና ፡
ሄኖክ ፡ ተሠውሮ ፡ ያየው ፡ በዚህ ፡ መላ ፡ ተፈ
ጸመ ።

# ወንጌል ዘማቴዎስ ፩

ወንጌል ቅዱስ ዘእግዚእነ ወመድኃኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ ። ብሥራተ ማቴዎስ ሐዋርያ አሐዱ እምዐሠርቱ ወክልኤቱ ሐዋርያት ።

### ምዕራፍ ፩ ፤

### ክፍል ፩ ፡ በእንተ ኍልቈ ትውልድ ።

፩ መጽሐፈ ልደቱ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወል
ደ ዳዊት ወልደ አብርሃም ።
፪ አብርሃም ወለዶ ለይስሐቅ ፡ ወይስሐቅ ወለዶ ለያዕ
ቆብ ፡ ወያዕቆብኒ ወለደ ይሁዳሃ ወአኀዊሁ ።
፫ ወይሁዳኒ ወለደ ፋሬስሃ ወዛራሃ እምትእማር ፡ ወፋ
ሬስኒ ወለደ ኤስሮምሃ ፡ ወኤስሮምኒ ወለደ አራምሃ ።
፬ ወአራምኒ ወለደ አሚናዳብሃ ፡ ወአሚናዳብኒ ወለደ
ነአሶንሃ ፡ ወነአሶንኒ ወለደ ሰልሞንሃ ።
፭ ወሰልሞንኒ ወለደ ቦኤዝሃ እምራኬብ ፡ ወቦኤዝኒ
ወለደ ኢዮቤድሃ እምነ ሩት ፡ ወኢዮቤድኒ ወለደ
ዕሤይሃ ።
፮ ወዕሤይኒ ወለደ ዳዊትሃ ንጉሠ ፡ ወዳዊትኒ ንጉሥ
ወለደ ሰሎሞንሃ እምነ ብእሲተ ኦርዮ ።
፯ ወሰሎሞንኒ ወለደ ሮብአምሃ ፡ ወሮብአምኒ ወለደ
አብያሃ ፡ ወአብያኒ ወለደ አሳፍሃ ።
፰ ወአሳፍኒ ወለደ ኢዮሳፍጥሃ ፡ ወኢዮሳፍጥኒ ወለደ
ኢዮራምሃ ፡ ወኢዮራምኒ ወለደ (አካዝያስሃ ፡ ወአካ
ዝያስኒ ወለደ ኢዮአስሃ ፡ ወኢዮአስኒ ወለደ አሜስ
ያስሃ ፡ ወአሜስያስኒ ወለደ (ኦዝያንሃ) ዘተሰምየ
አዛርያስ ።
፱ ወኦዝያንኒ ወለደ ኢዮአታምሃ ፡ ወኢዮአታምኒ ወለ
ደ አካዝሃ ፡ ወአካዝኒ ወለደ ሕዝቅያስሃ ።
፲ ወሕዝቅያስኒ ወለደ ምናሴሃ ፡ ወምናሴኒ ወለደ አሞ
ጽሃ ፡ ወአሞጽኒ ወለደ ኢዮስያስሃ ።
፲፩ ወኢዮስያስኒ ወለደ ኢኮንያንሃ ፡ ወአኀዊሁ አመ
ፍልሰተ ባቢሎን ።
፲፪ ወእምድኅረ ፍልሰተ ባቢሎን ኢኮንያንኒ ወለደ ሰላ
ትያልሃ ፡ ወሰላትያልኒ ወለደ ዘሩባቤልሃ ።
፲፫ ወዘሩባቤልኒ ወለደ አብዩድሃ ፡ ወአብዩድኒ ወለደ
ኤልያቄምሃ ፡ ወኤልያቄምኒ ወለደ አዛርሃ ።
፲፬ ወአዛርኒ ወለደ ሳዶቅሃ ፡ ወሳዶቅኒ ወለደ አኪምሃ ፡
ወአኪምኒ ወለደ ኤልዩድሃ ።
፲፭ ወኤልዩድኒ ወለደ አልአዛርሃ ፡ ወአልአዛርኒ ወለደ
ማትያንሃ ፡ ወማትያንኒ ወለደ ያዕቆብሃ ።

# የማቴዎስ ወንጌል ፩

የጌታችን የመድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ቅዱስ ወንጌል ከዐሥራ ሁለቱ ሐዋርያት አንዱ ሐዋርያው ማቴዎስ የጻፈው ወንጌል ።

### ምዕራፍ ፩ ፤

### ክፍል ፩ ፡ ስለ ትውልድ ቍጥር ።

የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ የትውልዱ መጽሐፍ ፡ ፩
የዳዊት ልጅ የአብርሃም ልጅ ። ሉቃ ፫ ፥ ፳፫ - ፴፰ ።
አብርሃም ይስሐቅን ወለደው ፡ ይስሐቅም ያዕቆብን ፪
ወለደው ፡ ያዕቆብም ይሁዳንና ወንድሞቹን ወለደ ።
ዘፍ ፳፩ ፥ ፫ - ፲፪ ።
ይሁዳም ከትእማር ፋሬስንና ዛራን ወለደ ፡ ፋሬስም ፫
ኤስሮምን ወለደ ፡ ኤስሮምም አራምን ወለደ ። ዘፍ
፴፰ ፥ ፳፱ ።
አራምም አሚናዳብን ወለደ ፡ አሚናዳብም ነአሶንን ፬
ወለደ ፡ ነአሶንም ሰልሞንን ወለደ ። ፩ ዜና መዋ
፪ ፥ ፲ ።
ሰልሞንም ከራኬብ ቦኤዝን ወለደ ፡ ቦኤዝም ከሩት ፭
ኢዮቤድን ወለደ ፡ ኢዮቤድም ዕሤይን ወለደ ። ሩት
፬ ፥ ፲፫ - ፳፪ ።
ዕሤይም ንጉሥ ዳዊትን ወለደ ፡ ንጉሥ ዳዊትም ከኦ ፮
ርዮ ሚስት ሰሎሞንን ወለደ ። ፪ ሳሙ ፲፪ ፥ ፳፬ ።
ሰሎሞንም ሮብአምን ወለደ ፡ ሮብአምም አብያን ወ ፯
ለደ ፡ አብያም አሳፍን ወለደ ። ፩ ዜና መዋ ፫ ፥ ፲ ።
አሳፍም ኢዮሳፍጥን ወለደ ፡ ኢዮሳፍጥም ኢዮራ ፰
ምን ወለደ ፡ ኢዮራምም አካዝያስን ወለደ ፡ አካዝያ
ስም ኢዮአስን ወለደ ፡ ኢዮአስም አሜስያስን ወለ
ደ ፡ አሜስያስም አዛርያስ የተባለ ኦዝያንን ወለደ ።
፩ ነገ ፲፭ ፥ ፳፬ ። ፩ ዜና መዋ ፫ ፥ ፲፩ ።
ኦዝያንም ኢዮአታምን ወለደ ኢዮአታምም አካዝን ፱
ወለደ ፡ አካዝም ሕዝቅያስን ወለደ ። ፩ ዜና መዋ
፫ ፥ ፲፫ ።
ሕዝቅያስም ምናሴን ወለደ ፡ ምናሴም አሞጽን ወ ፲
ለደ ፡ አሞጽም ኢዮስያስን ወለደ ። ፩ ዜና መዋ
፫ ፥ ፲፬ ።
ኢዮስያስም በባቢሎን ምርኮ ጊዜ ኢኮንያንንና ፲፩
ወንድሞቹን ወለደ ።
ከባቢሎን ምርኮም በኋላ ኢኮንያን ፡ ሰላትያልን ፲፪
ወለደ ፡ ሰላትያልም ዘሩባቤልን ወለደ ። ዕዝ ፫ ፥ ፪ ።
ዘሩባቤልም አብዩድን ወለደ ፡ አብዩድም ኤልያቄ ፲፫
ምን ወለደ ፡ ኤልያቄምም አዛርን ወለደ ።
አዛርም ሳዶቅን ወለደ ፡ ሳዶቅም አኪንን ወለደ ፡ አኪ ፲፬
ንም ኤልዩድን ወለደ ።
ኤልዩድም አልአዛርን ወለደ ፡ አልአዛርም ማትያንን ፲፭
ወለደ ፡ ማትያንም ያዕቆብን ወለደ ።

፲፮ ወያዕቆብሰ ወለደ ዮሴፍሃ ፈታሪሃ ለማርያም ዘእም
ኔሃ ተወልደ እግዚእ ኢየሱስ ዘተሰምየ ክርስቶስ ።

፲፯ ወኵሎንኬ ትውልድ እምአብርሃም እስከ ዳዊት
፲ወ፬ቱ ፡ ወእምዳዊት እስከ ፍልሰተ ባቢሎን ትው
ልድ ፲ወ፬ቱ ፡ ወእምፍልሰተ ባቢሎን እስከ ክር
ስቶስ ትውልድ ፲ወ፬ቱ ፡ ወኵሎንኬ ትውልድ
እምአብርሃም እስከ ክርስቶስ ትውልድ አርበዓ ወ
ክልኤቱ ።

ክፍል ፪ ፡ በእንተ ፅንሰቱ ወልደቱ ለክርስቶስ ።

፲፰ ወለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ፡ ከመዝ ውእቱ ልደ
ቱ ፡ ወሶበ ተፍኅረት እሙ ማርያም ለዮሴፍ ዘእንበለ
ይትራከቡ ተረክበት (ውስተ ማኅፀን) ፅንስተ እመን
ፈስ ቅዱስ ።
፲፱ ወዮሴፍሰ ፈታሪሃ እስመ ጻድቅ ውእቱ ኢፈቀደ ይክ
ሥታ ፡ አላ መከረ ጽሚተ ይኅድጋ ።
፳ ወእንዘ ዘንተ ይሔሊ ናሁ አስተርአዮ መልአከ እግ
ዚአብሔር በሕልም እንዘ ይብል ፡ ኦ ዮሴፍ ወልደ
ዳዊት ኢትፍራህ ነሢአታ ለማርያም ፍኅርትከ ፡ እስ
መ ዘይትወለድ እምኔሃ እመንፈስ ቅዱስ ውእቱ ።
፳፩ ወትወልድ ወልደ ወትሰምዮ ስሞ ኢየሱስሃ እስመ
ውእቱ ያድኅኖሙ ለሕዝቡ እምኃጢአቶሙ ።

፳፪ ወዝ ኵሉ ዘኮነ ከመ ይትፈጸም ዘተብህለ እምኀበ
እግዚአብሔር በነቢይ እንዘ ይብል ።
፳፫ "ናሁ ድንግል ትፀንስ ወትወልድ ወልደ ፡ ወይሰመይ
ስሙ አማኑኤል ዘበትርጓሜሁ እግዚአብሔር
ምስሌነ" ።
፳፬ ወተንሢአ ዮሴፍ እምንዋሙ ገብረ በከመ አዘዞ
መልአከ እግዚአብሔር ወነሥአ ለማርያም ፍኅርቶ።

፳፭ ወኢያእመራ እስከ አመ ወለደት ወልደ ዘበኵራ
ወጸውዐ ስሞ ኢየሱስሃ ።

ምዕራፍ ፪ ፡

ክፍል ፫ ፡ በእንተ ምጽአተ ሰብአ ሰገል ።

፩ ወተወሊዶ እግዚእ ኢየሱስ በቤተ ልሔም ዘይሁዳ
በመዋዕለ ሄሮድስ ንጉሥ ናሁ መጽኡ መሰግላን
እምብሔረ ጽባሕ ወበጽሑ ውስተ ኢየሩሳሌም ።
፪ እንዘ ይብሉ አይቴ ሀሎ ዘተወልደ ንጉሠ አይሁድ
እስመ ርኢነ ኮከቦ ዚአሁ በምሥራቅ ወመጻእነ ከመ
ንስግድ ሎቱ ።
፫ ወሰሚዖ ሄሮድስ ንጉሥ ደንገፀ ወተሀውከ ወኵላ
ኢየሩሳሌም ምስሌሁ ።
፬ ወአስተጋብኦሙ ለኵሎሙ ሊቃነ ካህናት ወለጸሐ

ያዕቆብም ክርስቶስ የተባለ ጌታ ኢየሱስ ከእስዋ ፲፮
የተወለደ የማርያም እጮኛ ዮሴፍን ወለደ ። ምዕ
፳፮ ፡ ፲፮ ።
ትውልድም ሁሉ ከአብርሃም እስከ ዳዊት ዐሥራ አ ፲፯
ራት ትውልድ ፡ ከዳዊትም እስከ ባቢሎን ምርኮ ዐ
ሥራ አራት ትውልድ ፡ ከባቢሎን ምርኮም እስከ
ክርስቶስ ዐሥራ አራት ትውልድ ነው ፡ ትውልድም
ሁሉ ከአብርሃም እስከ ክርስቶስ አርባ ሁለት ነው ።
ሉቃ ፫ ፡ ፳፫-፴፰ ።

ክፍል ፪ ፡ ስለ ክርስቶስ መፀነስና መወለድ ።

የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ልደት እንዲህ ነው ፡ ፲፰
እናቱ ማርያም ለዮሴፍ በታጨች ጊዜ በመንፈስ
ቅዱስ ፅንሳ ተገኘች ። ሉቃ ፩ ፡ ፴፭ ።

እጮኛዋ ዮሴፍ ግን ጻድቅ ነበረና ሊገልጻት አልወ ፲፱
ደደም ዝም ብሎ ሊተዋት አሰበ እንጂ ።
እርሱ ይህን ሲያስብ የእግዚአብሔር መልአክ በሕ ፳
ልም ታየው እንዲህ ሲል ፤ የዳዊት ልጅ ዮሴፍ ሆይ
ከእርስዋ የሚወለደው በመንፈስ ቅዱስ ነውና እጮ
ኛህ ማርያምን ለመውሰድ አትፍራ ። ቍ ፲፰ ።
ልጅም ትወልዳለች ስሙንም ኢየሱስ ትለዋለች ፳፩
ወገኖቹን ከኃጢአታቸው ያድናቸዋልና ። ሉቃ
፩ ፡ ፴፩ ።
ይህ ሁሉ የሆነ ከእግዚአብሔር ዘንድ በነቢይ እን ፳፪
ዲህ ሲል የተነገረው ይፈጸም ዘንድ ነው ።
እነሆ ድንግል ትፀንሳለች ልጅም ትወልዳለች ስሙ ፳፫
ንም አማኑኤል ይባላል ፡ ትርጓሜውም እግዚአብ
ሔር ከእኛ ጋር ማለት ነው ። ኢሳ ፯ ፡ ፲፬ ።
ዮሴፍም ከእንቅልፉ ተነሥቶ የእግዚአብሔር መል ፳፬
አክ እንዳዘዘው አደረገ ፡ እጮኛው ማርያምንም
ወሰዳት ።
የበኵር ልጅዋንም እስክ ወለደች ፡ ስሙንም ኢየ ፳፭
ሱስ ብለው እስኪጠሩት ድረስ አላወቃትም ።
ሉቃ ፪ ፡ ፯ ።

ምዕራፍ ፪ ፤

ክፍል ፫ ፡ ስለ ሰብአ ሰገል መምጣት ።

በንጉሡ በሄሮድስ ዘመን በይሁዳ ዕፃ ቤተ ልሔም ፩
ጌታ ኢየሱስ በተወለደ ጊዜ እነሆ ሰብአ ሰገል ከም
ሥራቅ ወደ ኢየሩሳሌም ደረሱ ። ሉቃ ፪ ፡ ፩-፯ ።
ኮከቡን በምሥራቅ አይተን እንሰግድለት ዘንድ መ ፪
ጥተናልና የተወለደው የአይሁድ ንጉሥ ወዴት ነው
እያሉ ። ዘኍ ፳፬ ፡ ፲፭-፲፯ ።
ንጉሡ ሄሮድስም በሰማ ጊዜ ደነገጠ ኢየሩሳሌምም ፫
በመላዋ ከእርሱ ጋር ደነገጠች ።
የካህናት አለቆችና የሕዝቡን ጸሐፊዎች ሁሉ ሰብ ፬

ፍተ ሕዝብ ወተስእሎሙ ወይቤሎሙ በአይቴ ይት
ወለድ ክርስቶስ ።
፭ ወይቤልዎ በቤተ ልሔም ዘይሁዳ እስመ ከማሁ ጽ
ሑፍ በነቢይ ።
፮ ወአንቲኒ ቤተ ልሔም ምድረ ኤፍራታ ኢትቴሐቲ
እምነገሥተ ይሁዳ እስመ እምኔኪ ይወጽእ ንጉሥ
ዘይርዕዮሙ ለሕዝብየ እስራኤል ።
፯ ወእምዝ ጸውዖሙ ሄሮድስ ለሰብአ ሰገል ጽሚተ
ወተጠየቀ እምኔሆሙ መዋዕሊሁ በዘአስተርአዮሙ
ኮከብ ።
፰ ወፈነዎሙ ኀበ ቤተ ልሔም ወይቤሎሙ ሐዊረክሙ
ተሰአሉ ጥዩቀ በእንተ ውእቱ ሕፃን ወእምከመ ረከ
ብክምዎ ግብኡ ኀቤየ ወዜንዉኒ ከመ እምጻእ አነሂ
ወእስግድ ሎቱ ።
፱ ወሰሚዖሙ እምኀበ ንጉሥ ሖሩ ወናሁ ኮከብ ዘር
እዩ እምሥራቅ ይመርሖሙ እስከ ሶበ አብጽሖሙ
ቤተ ልሔም ወቆመ መልዕልተ በዓት ኀበ ሀሎ
ሕፃን ።
፲ ወርእዮሙ ኮከበ ተፈሥሑ ፍሥሐ ዓቢየ ።
፲፩ ወበዊኦሙ ውስተ ቤት ረከብዎ ለሕፃን ምስለ ማር
ያም እሙ ወወድቁ ወሰገዱ ሎቱ ወአርኃዉ መዛግ
ብቲሆሙ ወአብኡ ሎቱ አምኃ ወርቀ ከርቤ ወስኂነ።

፲፪ ወነገሮሙ በሕልም ከመ ኢይግብኡ ኀበ ሄሮድስ
ወእንተ ካልእ ፍኖት ገብኡ ወሖሩ ብሔሮሙ ።

ክፍል ፬ ፡ በእንተ በአተ ሕፃን ውስተ ምድረ ግብፅ ።

፲፫ ወእምድኅረ ኀለፉ እሉ ናሁ መልአከ እግዚአብሔር
አስተርአዮ በሕልም ለዮሴፍ እንዘ ይብል ተን
ሥእ ወንሣእ ሕፃነ ወእሞ ወጐየይ ውስተ ብሔረ
ግብፅ ወሀሉ ህየ እስከ አመ እነግረከ እስመ ሀለዎ
ለሄሮድስ ይኅሥሥ ለሕፃን ከመ ይቅትሎ ።
፲፬ ወተንሢኦ ነሥአ ሕፃነ ወእሞ በሌሊት ወሖረ ውስ
ተ ግብፅ ።
፲፭ ወነበረ ህየ እስከ አመ ሞቱ ለሄሮድስ ከመ ይትፈ
ጸም ዘተብህለ እምኀበ እግዚአብሔር በነቢይ እንዘ
ይብል "እምግብፅ ጸዋዕክዎ ለወልድየ" ።

ክፍል ፭ ፡ በእንተ ቅትለተ ሕፃናት ።

፲፮ ወሶበ ርእየ ሄሮድስ ከመ ተሣለቁ ላዕሌሁ ሰብአ
ሰገል ተምዐ ጥቀ ወአዘዘ ሐራሁ ወፈነወ ይቅትሉ
ኵሎ ሕፃናተ ዘቤተ ልሔም ወዘውስተ ኵሉ አድ
ያሚሃ ዘ፪ኤ ዓመት ወዘይንእስኒ እምኔሁ በከመ ሐ
ሳበ መዋዕል ዘተጠየቀ እምኀበ ሰብአ ሰገል ።
፲፯ አሜሃ ተፈጸመ ዘተብህለ በኤርምያስ ነቢይ እንዘ
ይብል ።
፲፰ ቃል በራማ ተሰምዐ ብካይ ወሰቆቃው ወገዓር ወሕ

ሰበ ክርስቶስ በየት ይወለዳል ብሎ ጠየቃቸው ።

በይሁዳ ዕፃ በቤተ ልሔም ነው አሉት ፤ በነቢይ እን ፭
ዲህ ተብሎ ተጽፏልና ። ዮሐ ፯ ፡ ፵፪ ።
የኤፍራታ ዕፃ ቤተ ልሔም አንቺም ከይሁዳ ነገሥ ፮
ታት አታንስም ወገኖቼ እስራኤልን የሚጠብቅ ንጉ
ሥ ካንቺ ይወለዳልና ። ሚክ ፭ ፡ ፪ ። ፪ ሳሙ ፭ ፡ ፪ ።
ከዚህ በኋላ ሄሮድስ ሰብአ ሰገልን በሥውር ጠርቶ ፯
ኮከቡ የታየበትን ዘመን ከነሱ ተረዳ ።

ሄዳችሁ የዚያን ሕፃን ነገር እርግጡን መርምሩ ያገ ፰
ኛችሁትም እንደሆነ እኔም መጥቼ እሰግድለት ዘን
ድ በኔ በኩል ተመልሳችሁ ንገሩኝ ብሎ ወደ ቤተ
ልሔም ሰደዳቸው ።
የነገራቸውንም ሰምተው ከንጉሡ ሄዱ እነሆ በም ፱
ሥራቅ ያዩት ኮከብ ወደ ቤተ ልሔም እስኪ ያደር
ሳቸው ድረስ ይመራቸው ነበር ፤ ሕፃኑ ካለበትም
ዋሻ ላይ ደርሶ ቆመ ።
ኮከቡንም በዩ ጊዜ እጅግ ደስ አላቸው ። ፲
ወደ ቤተ ልሔምም በገቡ ጊዜ ሕፃኑን ከእናቱ ከማ ፲፩
ርያም ጋራ አገኙት ወድቀውም ሰገዱለት ሣጥናቸ
ውንም ከፍተው ወርቅ ከርቤ ዕጣን እጅ መንሻ አቀ
ረቡለት ። መዝ ፸፪ ፡ ፯ - ፲፭ ። ኢሳ ፷ ፡ ፮ - ፱ ።
ወደ ሄሮድስም እንዳይመለሱ በሕልም ነገራቸው በ ፲፪
ሌላ መንገድም ወደ አገራቸው ተመልሰው ገቡ ።

ክፍል ፬ ፡ ሕፃኑ ወደ ግብፅ ስለ መግባቱ ።

እነርሱም ከሄዱ በኋላ እነሆ ሄሮድስ ሕፃኑን ሊገ ፲፫
ድለው ይሻዋልና ተነሣ ፤ ሕፃኑንና እናቱን ይዘህ
ወደ ምድረ ግብፅ ሽሽ እስክነግርህም ድረስ ከዚያ
ኑር ብሎ የእግዚአብሔር መልአክ ለዮሴፍ በሕልም
ነገረው ።
እርሱም በሌሊት ተነሥቶ ሕፃኑንና እናቱን ይዞ ፲፬
ወደ ግብፅ ሄደ ።
ሄሮድስ እስኪሞት ድረስም በዚያ ኖረ ፤ ከእግዚአ ፲፭
ብሔር ዘንድ ልጄን ከግብፅ ጠራሁት ተብሎ በነ
ቢይ የተነገረው ይፈጸም ዘንድ ። ሆሴ ፲፪ ፡ ፩ ።

ክፍል ፭ ፡ ስለ ሕፃናት መገደል ።

ሄሮድስም ሰብአ ሰገል እንደ ተዘበበቱበት ባየ ጊዜ ፲፮
እጅግ ተቈጣና ከሰብአ ሰገል እንደተረዳው ዘመን
ልክ ሁለት ዓመት የሆናቸውን ፤ ከዚያም በታች የሆ
ነውን በቤተ ልሔምና በአውራጃዎቹ ሁሉ ያሉት
ሕፃናትን ይገድሉ ዘንድ ጭፍሮቹን አዝዞ ሰደደ ።
የዚያን ጊዜ እንዲህ ሲል በነቢይ በኤርምያስ የተነ ፲፯
ገረው ተፈጸመ ።
ራሄል ስለ ልጆቿ ስታለቅስ ብዙ መከራ ጩኸት ፤ ፲፰

ማም ብዙኅ፣ ራኄል እንዘ ትበኪ በእንተ ውሉዳ ወአበየት ተናዝዞ ወነጊፈ ላህ፣ እስመ ኢኮንዋ ውሉዳ ውሉደ ወኢሀለዉ ።

ክፍል ፯፡ በእንተ ሞተ ሄሮድስ ወግብአተ እግዚእነ ።

፲፱ ወመዊቶ ሄሮድስ ናሁ መልአከ እግዚአብሔር አስተርአዮ በሕልም ለዮሴፍ በብሔረ ግብፅ ።
፳ እንዘ ይብል ተንሥእ ወንሣእ ሕፃነ ወእሞ ወሑር ውስተ ምድረ እስራኤል እስመ ሞቱ እለ የኃሥሥዋ ለነፍሰ ዝ ሕፃን ።
፳፩ ወተንሢኦ ነሥአ ሕፃነ ወእሞ ወቦአ ውስተ ምድረ እስራኤል ።
፳፪ ወሰሚዖ ከመ አርኬላኦስ ነግሠ ለይሁዳ ህየንተ አቡሁ ሄሮድስ ፈርሃ ሐዊረ ህየ ወአስተርአዮ በሕልም ወተግሕሠ ውስተ ደወለ ገሊላ ።
፳፫ ወበጺሖ ኀደረ ውስተ ብሔር እንተ ስማ ናዝሬት ከመ ይብጻሕ ወይትፈጸም ዘተብህለ በነቢይ ከመ ናዝራዊ ይሰመይ ወልድየ ።

ምዕራፍ ፫ ።

ክፍል ፰፡ በእንተ ስብከተ ዮሐንስ መጥምቅ ።

፩ ወበውእቱ መዋዕል በጽሐ ዮሐንስ መጥምቅ እንዘ ይሰብክ በገዳመ ይሁዳ ዘዮርዳኖስ ።
፪ እንዘ ይብል ነስሑ እስመ ቀርበት መንግሥተ ሰማያት ።
፫ እስመ ዝንቱ ውእቱ ዘተብህለ በኢሳይያስ ነቢይ እንዘ ይብል ቃለ ዓዋዲ ዘይሰብክ በገዳም ወይብል ጺሑ ፍኖቶ ለእግዚአብሔር ወርቱዐ ግበሩ መጽያሕቶ ።
፬ ወልብሱ ለዮሐንስ ከነ እምፀጕረ ገመል ወቅናቱ ዘአዲም ውስተ ሐቌሁ ወሲሳዩ አንበጣ ወመዓረ ጸደና ።
፭ ወየሐውሩ ኀቤሁ ኵሎሙ ሰብአ ይሁዳ ወኢየሩሳሌም ወኵሉ አድያሚሃ ለዮርዳኖስ ።
፮ ወያጠምቆሙ ለኵሎሙ በፈለገ ዮርዳኖስ እንዘ ይትአመኑ ኃጣውኢሆሙ ።
፯ ወሶበ ርእየ ብዙኃነ አሕዛበ እምፈሪሳውያን ወእምሰዱቃውያን እንዘ ይመጽኡ ውስተ ጥምቀቱ ጽሚተ ይቤሎሙ አ ትውልደ አራዊተ ምድር መኑ አመረክሙ ትጕየዩ እመቅሠፍት ወእመንሱት ወእመዓት ዘይመጽእ ።
፰ ግበሩኬ እንከ ፍሬ ሠናየ ዘይደልወክሙ ለንስሓ ።
፱ ወኢይምሰልክሙ ዘታመስጡ በብሂለ አብ ብነ አብርሃም፣ እብለክሙ ከመ ይክል እግዚአብሔር እምእላንቱ አእባን አንሥኦ ውሉድ ለአብርሃም ።



ሙሾ፣ ለቅሶ፣ ዋይታ በራማ ተሰማ፣ ለቅሶ መተውን መጽናናትንም እንቢ አለች፣ ልጆቿ ልጆችን አልሆኗትምና የሉምና ። ኤር ፴፩ ፡ ፲፭ ።

ክፍል ፯፡ ስለ ሄሮድስ መሞትና ስለ ጌታችን መመለስ ።

ሄሮድስ በሞተ ጊዜ እነሆ የእግዚአብሔር መል ፲፱
አክ በግብፅ ሀገር ለዮሴፍ በሕልም ታየው ።
እንዲህ ሲል የሕፃኑን ነፍስ የሚሹ ሙተዋልና ፳
ተነሥተህ ሕፃኑንና እናቱን ይዘህ ወደ እስራኤል
ምድር ተመለስ ።
እርሱም ተነሥቶ ሕፃኑንና እናቱን ይዞ ወደ እስራ ፳፩
ኤል ምድር ገባ ።
አርኬላስም ባባቱ በሄሮድስ ፈንታ በይሁዳ እንደ ፳፪
ነገሠ በሰማ ጊዜ ወደዚያ ለመሄድ ፈራ በሕልምም
ተገልጦለት ወደ ገሊላ አገር ሄደ ።
ልጄ ናዝራዊ ይባላል ተብሎ በነቢይ የተነገረው ፳፫
ይፈጸም ዘንድ መጥቶ ናዝሬት በምትባል አገር
ኖረ ። ዘካ ፮ ፡ ፲፪ ። ዘመሳ ፲፫ ፡ ፭ - ፯ ።

ምዕራፍ ፫ ።

ክፍል ፰፡ ስለ መጥምቁ ዮሐንስ ስብከት ።

በዚያም ወራት መጥምቁ ዮሐንስ የዮርዳኖስ አው ፩
ራጃ በምትሆን በይሁዳ ምድረ በዳ እየሰበከ መጣ።
ማር ፩ ፡ ፩ - ፰ ። ሉቃ ፫ ፡ ፩ - ፩ ።
መንግሥተ ሰማያት ቀርባለችና ንስሐ ግቡ እያለ ። ፪
ምዕ ፬ ፡ ፲፯ ።
የእግዚአብሔርን መንገድ ጥረጉ ፡ ጥርጊያውንም ፫
አስተካክሉ ብሎ በምድረ በዳ የሚያስተምር አዋጅ
ነጋሪ ተብሎ በነቢዩ በኢሳይያስ የተነገረለት ይህ
ነውና ። ኢሳ ፵ ፡ ፫ ። ዮሐ ፩ ፡ ፳፫ ።
የዮሐንስም ልብሱ ከግመል ፀጕር የተሠራ ነበር፣ ፬
በወገቡም መታጠቂያው ቀለም የገባ ጠፍር ነበር፣
ምግቡም አንበጣና የጣዝማ ማር ነበር ። ፪ ነገ ፩ ፡ ፰ ።
በይሁዳ ፡ በኢየሩሳሌም ፣ በዮርዳኖስ አውራጃ ያሉ ፭
ሰዎች ሁሉ ወደ እርሱ ይሄዱ ነበር ።
ኃጢአታቸውንም እየተናዘዙ በዮርዳኖስ ወንዝ ሁሉ ፮
ንም ያጠምቃቸው ነበር ።
ነገር ግን ከፈሪሳውያንና ከሰዱቃውያን ወገን ከሕ ፯
ዝቡ ተቀላቅለው ወደ ጥምቀቱ ሲመጡ ብዙ ሰዎ
ችን በየ እናንተ የምድር አባብ ልጆች ከሚመ
ጣው ቁጣ ጥፋትና መቅሠፍት ትሸሹ ዘንድ ማን
አመለከታችሁ ። ምዕ ፳፫ ፡ ፴፫ ።
እንግዲያስ ለንስሐ የሚያበቃችሁን በጎ ሥራ ሥሩ ። ፰
አብርሃምን ያህል አባት አለን በማለት የምታመልጡ ፱
አይምሰላችሁ እግዚአብሔር ከእነዚህ ደንጎች ለአብ
ርሃም ልጅ አድርጎ ማስነሣት እንዲቻለው እነግራች
ኋለሁ ። ዮሐ ፰ ፡ ፴፫ - ፵፪ ። ሮሜ ፪ ፡ ፳፰ - ፳፱ ።

፲ እስመ ናሁ ወድአ ማኅፄ ተሠይመ ውስተ ጕንደ ዕፀው ይንበር ኵሉኬ ዕፅ ዘኢይፈሪ ፍሬ ሠናየ ይትገዘም ውስተ እሳት ይትወደይ ።

፲፩ አንሰኬ አጠምቀክሙ በማይ ለንስሓ ወዘይመጽእ እምድኅሬየ ውእቱ ይጸንዕ እምኔየ ዘኢይደልወኒ ዕፁር አሣዕኖ ወውእቱ ያጠምቀክሙ በመንፈስ ቅዱስ ወበእሳት ።

፲፪ ዘመስሔ ውስተ እዴሁ ዘቦቱ ያነጽሕ ዓውደ እክሉ ፡ ወያስተጋብእ ሥርናዮ ውስተ መዛግብቲሁ ወኀሠርሰ ያውዒ በእሳት ዘኢይጠፍእ ።

ክፍል ፰ ፡ በእንተ ጥምቀተ እግዚእነ ኢየሱስ ።

፲፫ አሜሃ መጽአ እግዚእ ኢየሱስ እምገሊላ ውስተ ዮርዳኖስ ከመ ይጠመቅ እምዮሐንስ በፈለገ ዮርዳኖስ ።

፲፬ ወዮሐንስሰ አበዮ እንዘ ይብል አነ እፈቅድ እምኀቤከ እጠመቅ ወአንተኑ ትመጽእ ኀቤየ ።

፲፭ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ ኅድግ ምዕረሰ እስመ ከመዝ ተድላ ለነ ወይደልወነ ከመ ንፈጽም ኵሎ ጽድቀ ወእምዝ ኃደጎ ።

፲፮ ወተጠሚቆ እግዚእ ኢየሱስ ሶቤሃ ወፅአ እማይ ወናሁ ተርኅወ ሎቱ ሰማይ ወርእየ መንፈሰ እግዚአብሔር እንዘ ይወርድ በአምሳለ ርግብ ወነበረ ዲቤሁ ።

፲፯ ወናሁ መጽአ ቃል እምሰማይ ዘይብል ዝንቱ ውእቱ ወልድየ ዘአፈቅር ዘቦቱ ሠመርኩ ።

ምዕራፍ ፬ ፤

ክፍል ፱ ፡ በእንተ ጾሙ ለእግዚእነ

ወተመከሮቱ እምዲያብሎስ ።

፩ ወእምዝ ወሰዶ መንፈስ ገዳመ ለእግዚእ ኢየሱስ ከመ ይትመከር እምኀበ ዲያብሎስ ።

፪ ወጾመ አርበዓ መዓልተ ወአርበዓ ሌሊተ ወእምድኅረዝ ርኅበ ።

፫ ወቀርበ ዘያሜክሮ ወይቤሎ እመሰ ወልደ እግዚአብሔር አንተ በል ከመ እላንቱ አእባን ኅብስተ ይኩና ።

፬ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ ጽሑፍ ከመ አኮ በኅብስት ከመ ዘየሐዩ ሰብእ አላ በኵሉ ቃል ዘይወጽእ እምአፉሁ ለእግዚአብሔር ።

፭ ወእምዝ ነሥኦ ዲያብሎስ ወወሰዶ ውስተ ቅድስት ሀገር ወአቀሞ ውስተ ተድባበ ቤተ መቅደስ ።

፮ ወይቤሎ እመሰ አማን ወልዱ ለእግዚአብሔር አንተ ቅንዕ እምዝየ ወተወረው ታሕተ ፤ እስመ ጽሑፍ ከመ ለመላእክቲሁ ይኤዝዞሙ በእንቲአከ ከመ ይዕ



እነሆ ምሳር በዛፎች ግንድ ላይ ሊወድቅ ተቃጥቶ አልና መልከም ፍሬ የማያፈራ ዛፍ ሁሉ ይቈረጣል ወደ እሳትም ይጣላል ። ሉቃ ፲፫ ፡ ፯ - ፱ ። ፲

እኔ ለንስሐ በውሃ አጠምቃችኋለሁ ጫማውን ለመሸከም የማይገባኝ ከኔ በኋላ የሚመጣው እርሱ ግን ከእኔ ይልቅ ይበረታል ፡ እርሱ በመንፈስ ቅዱስ በእሳት ያጠምቃችኋል ። ዮሐ ፩ ፡ ፳፯ - ፴፯ ። ፲፩

አውድማውን የሚያጠራበት መንሽ በእጁ ያለ ፡ ስንዴውንም በሪቅ በጐተራ ይሰበስባል ፡ ገለባውን ግን በማይጠፋ እሳት ያቃጥላል ። መዝ ፩ ፡ ፬ - ፲፩ ። ፲፪

ክፍል ፰ ፡ ስለ ጌታችን ስለ ኢየሱስ ጥምቀት ።

በዚያን ጊዜ ጌታ ኢየሱስ በዮሐንስ እጅ ፡ በዮርዳኖስ ወንዝ ይጠመቅ ዘንድ ከገሊላ ወደ ዮርዳኖስ ወደ ዮሐንስ መጣ ። ማር ፩ ፡ ፱ ። ሉቃ ፫ ፡ ፳፪ ። ዮሐ ፩ ፡ ፴፩ ። ፲፫

ዮሐንስ ግን እኔ ካንተ ልጠመቅ እሻለሁ ፡ አንተ ወደ እኔ ትመጣለህን ? ብሎ አይሆንም አለው ። ፲፬

ጌታ ኢየሱስም መልሶ እንዲህ ያለው ተድላ ደስታ ለእኛ ነውና እውነትንም ሁሉ ልንፈጽም ይገባናልና አንድ ጊዜስ ተው አለው ፡ ከዚህ በኋላ ተወው ። ፲፭

ጌታ ኢየሱስም ከተጠመቀ በኋላ ያን ጊዜውኑ ከውሀ ወጣ እነሆ ሰማይም ተከፈተለት ፡ የእግዚአብሔርም መንፈስ በርግብ አምሳል ወርዶ በራሱ ላይ ሲቀመጥ አየ ። ፲፮

እነሆ የምወደው በእርሱ ደስታዬን የማይበት ልጄ ይህ ነው ፡ የሚል ድምፅ ከሰማይ መጣ ። ኢሳ ፵፪ ፡ ፩ ። ፲፯

ምዕራፍ ፬ ።

ክፍል ፱ ፡ ስለ ጌታችን ጾምና

ከዲያብሎስ ስለ መፈተኑ ።

ከዚህም በኋላ መንፈስ ጌታ ኢየሱስን ወደ ምድረ በዳ ወሰደው ፡ ከዲያብሎስ ሊፈተን ። ማር ፩ ፡ ፲፪ - ፲፫ ። ሉቃ ፬ ፡ ፩ - ፲፫ ። ዕብ ፬ ፡ ፲፭ ። ፩

አርባ ቀን አርባ ሌሊትም ጾመ ፡ ከዚህም በኋላ ተራበ ። ዘፀ ፴፬ ፡ ፳፰ ። ፪

የሚፈታተነውም ቀርቦ አንተ የእግዚአብሔር ልጅ ከሆንክስ እነዚህ ድንጋዮች ዳቦ እንዲሆኑ እዘዝ አለው ። ፫

ጌታ ኢየሱስም መለሰ ፤ ሰው የሚድነው ከእግዚአብሔር አፍ በሚወጣው ቃል ነው እንጂ ፡ በእንጀራ እንዳይደለ ተጽፏል ። ዘዳግ ፰ ፡ ፫ ። ፬

ከዚህም በኋላ ዲያብሎስ ወደ ቅድስት ሀገር ወስዶ በቤተ መቅደሱ ጕልላት ላይ አቆመው ። ምዕ ፳፯ ፡ ፶፫ ። ፭

አንተ በእውነት የእግዚአብሔር ልጅ ከሆንክስ ከዚህ መር ብለህ ወደታች ውረድ ፡ በመንገድህ ይጠብቁህ ዘንድ ስለ አንተ መላእክትን እንዲአዝዛቸው ፮

ቀቡከ በኵሉ ፍናዊከ ወበእደዊሆሙ ያነሥኡከ
ከመ ኢትትዐቀፍ በዕብን እግረከ ።
፯ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ ካዕበ ጽሑፍ
ኢታመክሮ ለእግዚአብሔር አምላክከ ።

፰ ወእምዝ ነሥኦ ዲያብሎስ ወአዕረጎ ውስተ ደብር
ነዋህ ጥቀ ወአርአዮ መንግሥታተ ኵሉ ዓለም ወኵ
ሎ ክብሮ ።
፱ ወይቤሎ ዘንተ ኵሎ እሁበከ ለእመ ሰገድከ ሊተ
ወአማኅከኒ ።
፲ ወእምዝ ይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ሑር እምድኅሬየ
ሰይጣን ጽሑፍ ውእቱ ለእግዚአብሔር አምላክከ ት
ስግድ ወኪያሁ ባሕቲቶ ታምልክ ።
፲፩ ወእምዝ ኃደጎ ዲያብሎስ ወናሁ መጽኡ መላእክት
ይትለአክዎ ።

## ክፍል ፲ ፡ እምናዝሬት ኀበ ቅፍርናሆም ።

፲፪ ወሰሚዖ እግዚእ ኢየሱስ ከመ ዮሐንስ ተእኅዘ ተግ
ኅሠ ውስተ ደወለ ገሊላ ።
፲፫ ወኃደጋ ለናዝሬት ወመጺኦ ኃደረ ቅፍርናሆም እንተ
መንገለ ባሕር ውስተ አድባረ ዛብሎን ወንፍታሌም ።
፲፬ ከመ ይትፈጸም ዘተብህለ በኢሳይያስ ነቢይ እንዘ
ይብል ።
፲፭ ምድረ ዛብሎን ወምድረ ንፍታሌም ፍኖተ ባሕር
ማዕዶተ ሐይቀ ዮርዳኖስ (ጲራልዩ ወጲራልያስ) ወገ
ሊላ ዘአሕዛብ ።
፲፮ ሕዝብ ዘይነብር ውስተ ጽልመት ርእየ ብርሃነ ዓቢየ ፤
ወለእለሂ ይነብሩ ውስተ ጽልመት ወጽላሎተ ሞት
ብርሃን ሠረቀ ሎሙ ።

## ክፍል ፲፩ ፡ በእንተ ትምህርት ቀዳሚት ።

፲፯ ወእምአሜሃ አኀዘ እግዚእ ኢየሱስ ይስብክ ወይበል
ነስሑ እስመ ቀርበት መንግሥተ ሰማያት ።
፲፰ ወእንዘ ያንሶሱ መንገለ ባሕረ ገሊላ ርእየ ክልኤተ
አኀወ ስምዖንሃ ዘተሰምየ ጴጥሮስ ወእንድርያስሃ
እኁዋሁ እንዘ ይወድዩ መርበብቶሙ ውስተ ባሕር
እስመ መሠግራን እሙንቱ ።
፲፱ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ንዑ ትልዉኒ ወእሬስ
የክሙ ትኩኑ መሠግራነ ሰብእ ።
፳ ወበጊዜሃ ኃደጉ መሣግሪሆሙ ወተለውዎ ።
፳፩ ወተዓዲዎ ሕቀ እምህየ ርእየ ክልአነ ክልኤተ አኀወ
ያዕቆብሃ ወልደ ዘብዴዎስ ወዮሐንስሃ እኁዋሁ ውስ
ተ ሐመር ምስለ ዘብዴዎስ አቡሆሙ እንዘ ይሠርዑ
መያስተሣንዩ መሣግሪሆሙ ወጸውዖሙ ።
፳፪ ወበጊዜሃ ኃደጉ ሐመሮሙ ወዘብዴዎስሃ አባሆሙ
ወተለውዎ ።



ተጽፏልና እግርህንም በድንጊያ እንዳትሰነክል በእ
ጃቸው ያነሡሃልና አለው ። መዝ ፺፩ ፡ ፲፩ - ፲፪ ።
ጌታ ኢየሱስም መልሶ ዳግመኛ ፡ ፈጣሪህ እግዚአብ ፯
ሔርን አትፈታተነው ተብሎ ተጽፏል አለው ። ዘዳግ
፯ ፡ ፲፯ ።
ከዚህም በኋላ ዲያብሎስ እጅግ ረዥም ወደሆነ ተራ ፰
ራ አውጥቶ የዓለሙን ሁሉ መንግሥታት ክብሩንም
ሁሉ አሳየው ።
ብትሰግድልኝና እጅ ብትነሣኝ ይህን ሁሉ እሰጥ ፱
ሀለሁ አለው ።
ከዚህ በኋላ ጌታ ኢየሱስ አንተ ሰይጣን ከአጠገቤ ፲
ሒድ ለፈጣሪህ ለእግዚአብሔር ልትሰግድ እሱንም
ብቻ ልታመልክ ተጽፏል አለው ።
ከዚህ በኋላ ዲያብሎስ ተወው እነሆ መላእክትም ፲፩
ሊያገለግሉት መጡ ። ዮሐ ፩ ፡ ፶፩ ። ዕብ ፩ ፡ ፯ - ፲፱ ።

## ክፍል ፲ ፡ ከናዝሬት ወደ ቅፍርናሆም ።

ጌታ ኢየሱስም ዮሐንስ እንደ ተያዘ በሰማ ጊዜ ወደ ፲፪
ገሊላ አውራጃ ሔደ ። ምዕ ፲፬ ፡ ፫ ።
ናዝሬትንም ትቶ መጥቶ በዛብሎን በንፍታሌም አገ ፲፫
ሮች መከከል በምትገኝ በባሕር አጠገብ ባለች በቅፍ
ርናሆም ኖረ ።
በነቢዩ በኢሳይያስ ዘንድ እንዲህ ተብሎ የተነገረው ፲፬
ይፈጸም ።
የዛብሎን ምድርና የንፍታሌም ምድር የባሕሩ መን ፲፭
ገድ የዮርዳኖስ ወንዝ ወደብ (የገጠር መንደሮች)
አሕዛብ የሚኖሩበት ገሊላ ። ሉቃ ፯ ፡ ፯ ።
በጨለማ የሚኖር ሕዝብ ታላቅ ብርሃን አየ ፡ በጨ ፲፮
ለማ ፡ በሞት ጥላ ለነበሩ ብርሃን ወጣላቸው ። ኢሳ
፱ ፡ ፩ - ፫ ።

## ክፍል ፲፩ ፡ ስለ መጀመሪያዪቱ ትምህርት ።

ከዚያን ጊዜ ጀምሮ ጌታ ኢየሱስ መንግሥተ ሰማ ፲፯
ያት ቀርባለችና ንስሐ ግቡ እያለ ይሰብክ ጀመር ።
በገሊላ ባሕር ዳር ለዳር ሲመላለስም ሁለቱን ወንድ ፲፰
ማማቾች ጴጥሮስ የተባለ ስምዖንና ወንድሙ እንድር
ያስን መረባቸውን ወደ ባሕር ሲጥሉ አየ ፡ ዓሣ አጥ
ማጆች ነበሩና ። ማር ፩ ፡ ፲፮ - ፲፱ ። ሉቃ ፭ ፡ ፩ - ፲፩ ።
ጌታ ኢየሱስ ኑ ተከተሉኝና ሰውን የምታጠምዱ እን ፲፱
ድትሆኑ አደርጋችኋለሁ አላቸው ። ሕዝቅ ፵፯ ፡ ፲ ።
ወዲያውኑም መረባቸውን ትተው ተከተሉት ። ፳
ከዚያም ጥቂት እልፍ ብሎ ሌሎችን ሁለት ወንድማ ፳፩
ማች የዘብዴዎስ ልጅ ያዕቆብንና ወንድሙ ዮሐን
ስን ከባታቸው ከዘብዴዎስ ጋራ በታንኳ ሆነው መረ
ባቸውን ሲያበጁ ሲያጥቡ አየና ጠራቸው ።
ወዲያውኑ ታንኳቸውንና አባታቸው ዘብዴዎስን ት ፳፪
ተው ተከተሉት ።

<u>ክፍል ፲፪ ፡ በእንተ መንክራት</u>

<u>ዘተገብረ በላዕለ ድውያን ።</u>

፳፫ ወአንሶሰወ እግዚእ ኢየሱስ ውስተ ኵሉ ገሊላ እንዘ
ይሜህር በምኵራባቲሆሙ ወይሰብክ ወንጌለ መንግ
ሥት ወይፌውስ ኵሎ ደዌ ወኵሎ ሕማመ ዘውስተ
ሕዝብ ።
፳፬ ወወፅአ ስሙዓተ ነገሩ ውስተ ኵላ ሶርያ ወአምጽኡ
ኀቤሁ ኵሎ ሕሙማነ ወፅሁራነ ዘለለ ዚአሁ ሕማ
ሞሙ ወእለሂ በሙ አጋንንት ወወርኃውያነ ወእለሂ
ነገርጋር ወመፃጕዓነ ወአሕየዎሙ ።
፳፭ ወተለውዎ ብዙኃን አሕዛብ እምገሊላ ወእምዐሥሩ
አህጉር ወእምኢየሩሳሌም ወእምይሁዳ ወእማዕዶተ
ዮርዳኖስ ።

ምዕራፍ ፭ ፤

<u>ክፍል ፲፫ ፡ በእንተ ብፁዓን ።</u>

፩ ወሶበ ርእየ ብዙኃነ አሕዛበ ዓርገ ውስተ ደብር ወነ
በረ ወቀርቡ ኀቤሁ አርዳኢሁ ።
፪ ወከሠተ አፉሁ ወመሀሮሙ እንዘ ይብል ።
፫ ብፁዓን ነዳያን በመንፈስ እስመ ሎሙ ይእቲ መንግ
ሥተ ሰማያት ።
፬ ብፁዓን እለ ይላህዉ ይእዜ እስመ እሙንቱ ይትፌ
ሥሑ ።
፭ ብፁዓን የዋሃን እስመ እሙንቱ ይወርስዋ ለምድር ።
፮ ብፁዓን እለ ይርኅቡ ወይጸምኡ በእንተ ጽድቅ
እስመ እሙንቱ ይጸግቡ ።
፯ ብፁዓን መሐርያን እስመ ሎሙኒ ይምሕርዎሙ ።
፰ ብፁዓን ንጹሐነ ልብ እስመ እሙንቱ ይሬእይዎ ለእ
ግዚአብሔር ።
ብፁዓን ገባርያነ ሰላም እስመ እሙንቱ ውሉደ እግ
ዚአብሔር ይሰመዩ ።
፲ ብፁዓን እለ ይሰደዱ በእንተ ጽድቅ እስመ ሎሙ
ይእቲ መንግሥተ ሰማያት ።
፲፩ ብፁዓን አንትሙ ሶበ ይሰድዱክሙ ወይዘነጕጉክሙ
ወይነቡ ኵሎ እኩየ ላዕሌክሙ እንዘ ይሔስዉ በእ
ንቲአየ ።
፲፪ ተፈሥሑ ወተኀሠዩ እስመ ብዙኅ ዕሤትክሙ በሰ
ማያት እስመ ከማሁ ሰደድዎሙ ለነቢያት እለ እም
ቅድሜክሙ ።

<u>ክፍል ፲፬ ፡ በእንተ ግብር ወንጌላዊ ።</u>

፲፫ አንትሙ ውእቱ ፄዉ ለምድር ወእመሰ ፄው ለስሐ
በምንት እንከ ይቄስምዎ አልቦኬ እንከ ዘይበቍዕ



<u>ክፍል ፲፪ ፡ በሕሙማን ላይ</u>

<u>ስለ ተደረገው ተአምራት ።</u>

ጌታ ኢየሱስም በምኵራባቸው እያስተማረ መንግ ፳፫
ሥቱን የምትናገር ወንጌልን እየሰበከ ፡ በሕዝብም
የተናኘውን ሕማምና ደዌ እየፈወሰ በመላው ገሊላ
ተመላለሰ። ሉቃ ፬ ፡ ፲፭ - ፴፩ ። ግብ ሐዋ ፲ ፡ ፴፰ - ፬ ።
ወሬውም በመላው ሶርያ ተዳረሰ ፡ የታመሙትን ፳፬
የተጨነቁትን ሕመማቸው ልዩ ልዩ የሆነባቸውን
ወር እያየ የሚያማቸውን የጸናባቸውን ኵሉ አመ
ጡስትና አዳናቸው ። ማር ፮ ፡ ፶፮ - ፮ ።
ብዙ ሰዎችም ከገሊላ ከዐሥሩ አህጉር ከኢየሩሳሌም ፳፭
ከይሁዳ ከዮርዳኖስ ማዶ ተወጣጥተው ተከተሉት ።

ምዕራፍ ፭ ፣

<u>ክፍል ፲፫ ፡ ስለ ብፁዓን ።</u>

ብዙ ሕዝብ በየ ጊዜም ወደ ተራራ ወጥቶ ተቀመጠ ፩
ደቀ መዛሙርቱም ወደ እርሱ ቀረቡ ። ሉቃ ፮ ፡ ፩ ።
አፉንም ከፈተ ፡ እንዲህም ብሎ አስተማራቸው ። ፪
ዐውቀው ነዳያን የሆኑ ብፁዓን ናቸው ፡ መንግሥተ ፫
ሰማያት የነርሱ ናትና ። ኢሳ ፶፯ ፡ ፲፭ ።
ዛሬ የሚያዝኑ ብፁዓን ናቸው ደስ ይላቸዋልና ። ፬
መዝ ፻፳፮ ፡ ፭ ። ኢሳ ፷፩ ፡ ፪ ። ራእ ፯ ፡ ፲፯ ።
ቂም የማይዙ ብፁዓን ናቸው ፡ እነርሱ ምድርን ፭
ይወርሳሉና ። መዝ ፴፯ ፡ ፲፩ ።
ስለ ጽድቅ የሚራቡ የሚጸሙም ብፁዓን ናቸው ፡ ፮
እነርሱ ይጸግባሉና ። ኢሳ ፵፩ ፡ ፲፯ - ፶፩ ።
የሚራሩ ብፁዓን ናቸው ፡ ለነርሱም ይራሩላቸዋል ። ፯
ምዕ ፳፭ ፡ ፴፭ ። ያዕ ፪ ፡ ፲፫ ።
ልባቸው ንጹሕ የሆነላቸው ብፁዓን ናቸው ፡ እነርሱ ፰
እግዚአብሔርን ያዩታልና ። ፩ ዮሐ ፫ ፡ ፪ - ፫ ።
ዕርቅ የሚያደርጉ ብፁዓን ናቸው ፡ እነርሱ የእግዚአብ ፱
ሔር ልጆች ይባላሉና። ዕብ ፲፪ ፡ ፲፬ ። መዝ ፴፬ ፡ ፲፬ ።
ስለ ጽድቅ የሚሰደዱ ብፁዓን ናቸው ፡ መንግሥተ ፲
ሰማያት የእነርሱ ናትና ። ፩ ጴጥ ፫ ፡ ፲፬ ። ፪ ጢሞ
፪ ፡ ፲፪ ።
ቢአሳድዱአችሁ ፡ ቢአሽሟጥጧችሁ ስለ እኔም እየ ፲፩
ዋሹ ክፉ ነገርን ቢናገሩባችሁ ብፁዓን ናችሁ ።
፩ ጴጥ ፬ ፡ ፲፬ ። ኢሳ ፶፩ ፡ ፯ - ፰ ።
ደስ ይበላችሁ ዋጋችሁ በሰማይ ብዙ ነውና ፡ ከእና ፲፪
ንተ አስቀድሞ የነበሩ ነቢያትንም እንዲሁ አሳድደ
ዋቸው ነበርና ። ያዕ ፭ ፡ ፲ ። ዕብ ፲፩ ፡ ፳፭ - ፵ ።

<u>ክፍል ፲፬ ፡ ስለ ወንጌላዊ ሥራ ።</u>

የምድር ጨው እናንተ ናችሁ ፡ ጨው አልጫ ከሆነ ፲፫
እንግዲህ በምን ያጣፍጡታል ? እንግዲህ የሚጠ

ዘእንበለ ዘይገድፍዎ አፍአ ወይከይድዎ ሰብእ በእ
ገሪሆሙ ።

፲፬ አንትሙ ውእቱ ብርሃኑ ለዓለም ኢትክል ተከብቶ
ሀገር እንተ ተሐንፀት መልዕልተ ደብር ።

፲፭ ወኢያኀትዉ ማኅቶተ ከመ ያንብርዋ ታሕተ ከፊር
አላ ያነብርዋ ዲበ ተቅዋማ ወታበርህ ለኵሎሙ
እለ ውስተ ቤት ።
፲፮ ከማሁኬ ይብራህ ብርሃንክሙ በቅድመ ሰብእ ከመ
ይርአዩ ምግባሪክሙ ሠናየ ወይሰብሕዎ ለአቡክሙ
ዘበሰማያት ።

<u>ክፍል ፲፭ ፡ በእንተ አጽንዖተ ብሉይ ኪዳን ።</u>

፲፯ ኢይምሰልክሙ ዘመጻእኩ እሥዓሮሙ ለኦሪት ወለ
ነቢያት ዘእንበለ ዳእሙ ከመ እፈጽሞሙ ።
፲፰ አማን እብለክሙ እስከ አመ የኃልፍ ሰማይ ወም
ድር የውጣ እንተ አሐቲ ኅርመታ ወአሐቲ ቅርፀታ
ኢተኃልፍ እምኦሪት ወእምነቢያት እስከ ሶበ ኵሉ
ይትገበር ወይከውን ።
፲፱ ዘኬ ፈትሐ አሐተ እምእላ ትእዛዛት እንተ ተሐጽጽ
ወይሜህር ከመዝ ለሰብእ ሕፁፀ ይከውን በመንግ
ሥተ ሰማያት ወዘሰ ይገብር ወይሜህር ከመዝ ውእ
ቱ ዓቢየ ይከውን በመንግሥተ ሰማያት ።

፳ ናሁ እብለክሙ ከመ ለእመ ኢፈድፈደ ጽድቅክሙ
ፈድፋደ እምጸሐፍት ወእምፈሪሳውያን ኢትበውኡ
መንግሥተ ሰማያት ።

<u>ክፍል ፲፮ በእንተ ስድስቱ ቃላት ።</u>

፳፩ ሰማዕክሙ ዘተብህለ ለቀደምትክሙ ኢትቅትል ነፍሰ
ወዘሰ ቀተለ ነፍሰ ረስሐ ውእቱ ለኵነኔ ።

፳፪ ወአንሰ እብለክሙ ኵሉ ዘያምዕዕ እኀዋሁ በከንቱ
ረስሐ ውእቱ ለኵነኔ ወዘሂ ይቤሎ ለእኁሁ ኅሡር
ዘፀርቅ ረስሐ ወይትኴነን በዓውድ ፡ ወዘሂ ይቤሎ
ዐብድ ረስሐ ውእቱ ወይትኴነን በእሳተ ገሃነም ።

፳፫ ወእምከመኬ ታበውእ መባእከ ውስተ ምሥዋዕ
ወበህየ ተዘከርከ ከመበ እኁከ ዘተሐየሰከ ።
፳፬ ኅድግ ህየ መባአከ ቅድመ ምሥዋዕ ወሑር ቅድመ
ተኳነን ምስለ እኁከ ወእምዝ ገቢአከ አብእ
መባአከ ።
፳፭ ኩን ጠቢበ ለዕድውከ ፍጡነ እንዘ ሀሎከ ምስሌሁ
ውስተ ፍኖት ከመ ኢይመጡከ ዕድውከ ለመኰንን
ወመኰንን ይሚጥወከ ለወዓሊሁ ፡ ወወዓሊሁ ይሞ
ቅሐከ ።



ቅም አይደለም ፡ ሰዎች ወደ ውጭ አውጥተው ይጥ
ሉታል ፡ በእግራቸውም ይጠቀጥቁታል እንጂ ። ማር
፱ ፡ ፶ ። ሉቃ ፲፬ ፡ ፴፬ ።
የዓለም ብርሃኑ እናንተ ናችሁ ፡ በተራራ ላይ የተሠ ፲፬
ራች መንደር መሰወር አይቻላትም ። ዮሐ ፰ ፡ ፲፪ ።
ፊልጵ ፪ ፡ ፲፭ ።
ዕንቅብ ሊደፉበት ፡ መብራትን አያበሩም በመቅረ ፲፭
ዝዋ ላይ አኑረዋት በቤት ላሉት ሁሉ ታበራለች
እንጂ ። ማር ፬ ፡ ፳፩ ።
እንዲሁም ብርሃናችሁ በሰው ፊት ይብራ መልካሙ ፲፮
ሥራችሁን አይተው በሰማይ ያለው አባታችሁን
ያመሰግኑት ዘንድ ። ፩ ጴጥ ፪ ፡ ፲፪ ።

<u>ክፍል ፲፭ ፡ ስለ ብሉይ ኪዳን መጽናት ።</u>

ኦሪትን ነቢያትን ልሽራቸው የመጣሁ አይምሰላችሁ ፲፯
ላጸናቸው ነው እንጂ ። ምዕ ፫ ፡ ፲፭ ። ሮሜ ፫ ፡ ፴፪ ።
እውነት እላችኋለሁ አሠራረዟዋ አንዲት አቀራረ ፲፰
ፅዋ አንዲት የምትሆን የውጣ ሰማይ ምድር እስኪ
ያልፍ ፡ ሁሉም እስኪሆን እስኪደረግ ድረስ ከኦሪት
ከነቢያት ተለይታ አታልፍም ። ሉቃ ፲፮ ፡ ፲፯ ።
ከነዚህም ትእዛዛት ታንሳለች ብሎ የሚያስተምር ፲፱
አንዲቱን የሻረ ለሰውም እንዲህ ብሎ የሚያስተ
ምር በመንግሥተ ሰማይ የተለየ ይሆናል የሚያስተ
ምር ግን እርሱ በመንግሥተ ሰማይ ታላቅ ይሆናል።
ያዕ ፪ ፡ ፱ ። ዕዝ ፪ ፡ ፲ ።
አሁንም ጽድቃችሁ ከጻፎችና ከፈሪሳውያን ካልበ ፳
ለጠ ወደ መንግሥተ ሰማይ እንደማትገቡ እነግራች
ኋለሁ ።

<u>ክፍል ፲፮ ፡ ስለ ስድስቱ ቃላት ።</u>

አትግደል ነፍስ የገደለ በደለ ፡ እርሱ ፍርድ የሚገ ፳፩
ባው ነው የተባለውን ሰምታችኋል ። ዘፀ ፳ ፡ ፲፫ ።
ዘሌ ፳፬ ፡ ፲፯ ። ዘዳ ፲፯ ፡ ፰ ።
እኔ ግን ወንድሙን በከንቱ የሚያሳዝን ሰው በደለ ፳፪
እርሱ ለቅጣት ነው ፡ ወንድሙን ጐስቋላ ጨርቅ ለባ
ሽ ያለውም በደለ ፡ በአደባባይ ይፈረድበታል ደን
ቆሮ ያለውም በደለ በገሃነመ እሳት ይፈረድበታል
እላችኋለሁ ። ዮሐ ፫ ፡ ፲፭ ። ኢሳ ፳፯ ፡ ፳፬ ።
መባህን በመሠዊያው በምታቀርብበት ጊዜ በዚያም ፳፫
የተጣላህ ወንድምህ እንዳለ ብታስብ። ማር ፲፩ ፡ ፳፭ ።
መባውን ከዚያ ከመሠዊያው ፊት አኑረህ ሒድ አስ ፳፬
ቀድመህ ከወንድምህ ጋር ታረቅ ከዚህ በኋላ ተመ
ልሰህ መባህን አግባ ።
በመንገድ ከርሱ ጋር ሳለህ በባላጋራህ ቶሎ ዕወቅ ፳፭
በት ባላጋራህ ለዳኛ እንዳይሰጥህ ፡ ዳኛውም አሳ
ልፎ ለሎሌው ይሰጥሃል ሎሌውም ያስርሃል ።

፳፮ አማን እብለከ ከመ ኢትወፅእ እምህየ እስከ ሶበ ትሴለጥ ደኃሪተ ገመስ ዘላዕሌከ ።
፳፯ ሰማዕክሙ ዘተብህለ ለቀደምትክሙ ኢትዘሙ ።
፳፰ ወአንሰ እብለክሙ ኵሉ ዘርእያ ለብእሲት ወፈተዋ ወድአ ዘመወ ባቲ በልቡ ።
፳፱ ወእመኒ ዓይንከ ዘየማን ታስሕተከ ምልሓ ወግድፋ እምላዕሌከ እስመ ይሔይሰከ ነቋረከ ትባእ ውስተ መንግሥተ ሰማያት እምትባእ ምስለ ክልኤሆን አዕይንቲከ ውስተ እሳተ ገሃነም ።
፴ ወእመኒ እዴከ ዘየማን ታስሕተከ ምትራ ወግድፋ እምላዕሌከ እስመ ይሔይሰከ ይትኃጐል አሐዱ እምነ አባልከ እምኵሉ ሥጋከ ይትወደይ ውስተ ገሃነም ። እመኒ እግርከ ዘየማን ታስሕተከ ምትራ ወግድፋ እምላዕሌከ እስመ ይሔይሰከ ሐንካሰከ ትባእ ውስተ መንግሥተ ሰማያት እምትባእ ምስለ ክልኤሆን አእጋሪከ ውስተ ገሃነም ።
፴፩ ሰማዕክሙ ዘተብህለ ለቀደምትክሙ ኵሉ ዘይድኅር ብእሲቶ ይጽሐፍ ላቲ መጽሐፈ ኅዳጋቲሃ የሀባ ወይድኃራ ።
፴፪ ወአንሰ እብለክሙ ኵሉ ዘይድኅር ብእሲቶ ዘእንበለ ትዘሙ በላዕሌሁ ለሊሁ ረሰያ ዘማ ወዘሂ ኅድግተ አውሰበ ዘመወ ።
፴፫ ወካዕበ ሰማዕክሙ ዘተብለ ለቀደምትክሙ ኢትምሐሉ በሐሰት ወበሐቅ አግብኡ መሐላክሙ ለእግዚአብሔር ።
፴፬ ወአንሰ እብለክሙ ኢትምሐሉ ግሙራ ኢበሰማይ እስመ መንበሩ ለእግዚአብሔር ውእቱ ።
፴፭ ወኢበምድር እስመ መከየደ እገሪሁ ይእቲ ፡ ወኢበ ኢየሩሳሌም እስመ ሀገሩ ይእቲ ለንጉሥ ዓቢይ ።
፴፮ ወኢበርእስክሙ ኢትምሐሉ ወኢበሥእርተ ርእስክሙ እስመ ኢትክሉ አሐተ እምሥእርተ ርእስክሙ ኢአፃዕድዎ ወኢአጽልሞ ።
፴፯ ወይኩን ባሕቱ ነገርክሙ አሐደ ፡ እመሂ እወ እወ ወእመሂ አልቦ አልቦ ወፈድፋደሰ እምእሉ እምእኩይ ውእቱ ።
፴፰ ሰማዕክሙ ዘተብህለ ለቀደምትክሙ ዓይን ቤዛ ዓይን ወስን ቤዛ ስን ።
፴፱ ወአንሰኬ እብለክሙ ኢትትቃወምዎ ለእኩይ በእኩይ ወለዘሂ ጸፍዐከ መልታሕቴከ እንተ የማን ሚጥ ሎቱ ክልእታሂ ።
፵ ወለዘሂ ይፈቅድ ይትዐገልከ መልበሰከ ኅድግ ሎቱ ክዳነከሂ ።

ያለችሁን የሳንቲም ቅንስናሽ እስክትጨርስ ድረስ ከዚያ እንደማትወጣ በእውነት እነግርሃለሁ ። ፳፮
ከእናንተ አስቀድሞ ለነበሩ ሰዎች አታመንዝር የተባለውን ሰምታችኋል ። ዘፀ ፳ ፡ ፲፬ ። ፳፯
እኔ ግን ሴትን አይቶ የተመኛት ሁሉ በልቡ ፈጽሞ አመነዘረበት ብዬ እነግራችኋለሁ ። ኢዮ ፴፩ ፡ ፩ ። ፪ ጴጥ ፪ ፡ ፲፬ ። ፳፰
ቀኝ ዓይንህ ብታስትህ ከንተ አውጥተህ ጣላት ፡ ሁለት ዓይና ሆነህ ወደ ገሃነም እሳት ከምትገባ አንድ ዓይና ሆነህ ወደ መንግሥተ ሰማያት ብትገባ ይሻልሃልና ። ቈላ ፫ ፡ ፭ ። ምዕ ፲፰ ፡ ፱ ። ፳፱
ቀኝ እጅህም ብታስትህ ከንተ ላይ ቈርጠህ ጣላት አካልህ ሁሉ ወደ ገሃነም ከሚገባ አንዱ አካልህ ቢጠፋ ይሻላልና ፤ ቀኝ እግርህ ብታስትህ ከንተ ላይ ቈርጠህ ጣላት ፡ ሁለት እግር ሆነህ ወደ ገሃነም ከምትገባ አንድ እግር ሆነህ መንግሥተ ሰማይ ብትገባ ይሻልሃልና ። ፴
ከናንተ አስቀድሞ ለነበሩ ሰዎች ሚስቱን የሚፈታ ሰው ሁሉ የምትፈታበትን ደብዳቤ ጽፎ ይስጥና ይፍታት የተባለውን ሰምታችኋል ። ምዕ ፲፱ ፡ ፫ - ፱ ። ዘዳግ ፳፬ ፡ ፩ ። ፴፩
እኔ ግን ፤ ሳትሴስንበት ሚስቱን የሚፈታ ሁሉ እርሱ ራሱ ዘማ አደረጋት የተፈታችውንም ያገባ አመነዘረ ብዬ እነግራችኋለሁ ። ሉቃ ፲፯ ፡ ፲፰ ። ፩ ቆሮ ፯ ፡ ፲ ። ፴፪
ዳግመኛ ከእናንተ አስቀድሞ ለነበሩ ሰዎች መሐላችሁን በእግዚአብሔር ማሉ እንጂ በጣዖት አትማሉ የተባለውን ሰምታችኋል ። ዘፀ ፳ ፡ ፯ ። ዘሌ ፲፱ ፡ ፲፪ ። ፴፫
እኔ ግን ፈጽሞ አትማሉ እላችኋለሁ በሰማይም ቢሆን የእግዚአብሔር ዙፋኑ ነውና ። ኢሳ ፷፮ ፡ ፩ ። ግብ ሐዋ ፯ ፡ ፵፱ ። ፴፬
በምድርም ቢሆን የእግሩ መመላለሻ ናትና በኢየሩሳሌምም ቢሆን የታላቁ ንጉሥ ሀገር ናትና ። መዝ ፵፰ ፡ ፪ ። ፴፭
በራሳችሁም አትማሉ ፤ በራስ ጠጕራችሁም ቢሆን ከራስ ጠጕራችሁ አንዲቱን ነጭ ማድረግ ወይም ጥቁር ማድረግ አትችሉምና ። ፴፮
ነገራችሁ አንድ ይሁን እንጂ ቢኖር አለ ባይኖር የለም ከእነዚህ የወጣ ግን ከክፉ ወገን ነው ። ፪ ቆሮ ፩ ፡ ፲፯ ። ያዕ ፭ ፡ ፲፪ ። ፴፯
ከእናንተ አስቀድሞ ለነበሩ ሰዎች ዐይን ቢጠፋ ዐይን ይጥፋ ጥርስ ቢሰበር ጥርስ ይሰበር የተባለውን ሰምታችኋል ። ዘፀ ፳፩ ፡ ፳፫ - ፳፬ ። ዘሌ ፳፬ ፡ ፳ ። ፴፰
እኔ ግን ክፉን በክፉ አትቃወሙት እላችኋለሁ ፡ ቀኝ ፊትህን ለመታህ ግራ ፊትህን መልስለት ። ሉቃ ፮ ፡ ፳፱ ። ዘሌ ፲፱ ፡ ፲፰ ። ፴፱
መጐናጸፊያህን ሊቀማህ ለሚሻ ቀሚስህንም ተውለት ። ፵

፳፬ ወአንከሩ አርዳኢሁ በንተ ነገሩ ወካዕበ ይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ለአርዳኢሁ ደቂቅየ እፎ ዕፁብ ለእለ ቦሙ ንዋይ በዊእ ውስተ መንግሥተ እግዚአብሔር ።

፳፭ ይቀልል ይኅልፍ ገመል እንተ ቀዳዳ ሐጽ እምባዕል ይባእ ውስተ መንግሥተ እግዚአብሔር ።

፳፮ ወፈድፋደ አንከሩ ወተባሀሉ በበይናቲሆሙ መኑ እንከ ይክል ድኅነ ።

፳፯ ወነጸሮሙ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ በኀበ ሰብእ ኢይትከሀል ዝ ወበኀበ እግዚአብሔርሰ ኵሉ ይትከሀል ።

## ክፍል ፺ወ፯ ፤ በእንተ ዕሤቶሙ ለእለ ይተልውዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ።

፳፰ ወአኀዘ ጴጥሮስ ይበሉ ፤ ናሁ ንሕነ ኀደግነ ኵሎ ወተለውናከ ።

፳፱ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ አማን እብለክሙ አልቦ ዘየኀድግ አብያተ ፤ ወአኀወ ፤ ወአኃተ ፤ አበ ፤ ወእመ ፤ ብእሲተ ፤ ወውሉደ ፤ ወገራውሀ በእንቲአየ ወበእንተ ወንጌል ።

፴ ዘኢይትዐሠይ ምእተ ምክዕቢተ በዝንቱ ዓለም አብያተ ወገራውሀ ወአኀወ ወአኃተ ወአበ ወእመ ወውሉደ በስደት ወበዓለምሰ ዘይመጽእ ሕይወተ ዘለዓለም ።

፴፩ ወብዙኃን ቀደምት ይከውኑ ደኃርተ ፤ ወደኃርትኒ ይከውኑ ቀደምተ ።

## ክፍል ፺ወ፰ ፤ በእንተ ሕማማቲሁ ወሞቱ ።

፴፪ ወበፍኖት እንዘ የዐርጉ ኢየሩሳሌም ይቀድሞሙ እግዚእ ኢየሱስ ወደንገፁ ወእለሂ ይተልውዎ ፈርሁ ወነሥአሙ ለዐሠርቱ ወክልኤቱ ወአኀዘ ይንግሮሙ ዘሀለዎ ይርከቦ ።

፴፫ ወይቤሎሙ ናሁ ነዐርግ ኢየሩሳሌም ወይእኅዝዎ ለወልደ እጓለ እመሕያው ሊቃነ ካህናት ወጸሐፍት ወይኬንንዎ በሞት ወይሜጥውዎ ለአሕዛብ ።

፴፬ ወይሣለቁ ላዕሌሁ ወይጸርቅዎ ፤ ወይቀሥፍዎ ፤ ወይቀትልዎ ፤ ወይትነሣእ በሣልስት ዕለት ።

## ክፍል ፺ወ፱ ፤ በእንተ ደቂቀ ዘብዴዎስ

፴፭ ወእንዘ የሐውሩ ምስሌሁ ያዕቆብ ወዮሐንስ ክልኤሆሙ ደቂቀ ዘብዴዎስ ይቤልዎ ሊቅ ንፈቅድ ትግበር ለነ ዘሰአልናከ ።

ደቀ መዛሙርቱም ይህን ነገር አደነቁ ዳግመኛም ጌታ ኢየሱስ ለደቀ መዛሙርቱ እንዲህ አላቸው ፤ ልጆቼ ! ገንዘብ ላላቸው ሰዎች ወደ እግዚአብሔር መንግሥት መግባት እንዴት ጭንቅ ነው አላቸው ። መዝ ፷፪ ፲፩ ። ፩ ጢሞ ፮ ፲፯ ። ፳፬

ባለጸጋ ወደ እግዚአብሔር መንግሥት ከሚገባ ግመል የቀስት ጕጣት በሚያልፍበት ቀዳዳ ቢያልፍ ይቀላል ። ፳፭

እጅግም አደንቀው እርስ በርሳቸው ማን ሊድን ይችላል ? ተባባሉ ። ፳፮

ጌታ ኢየሱስም አያቸውና በሰው ዘንድ ይህ አይቻልም በእግዚአብሔር ዘንድ ግን ሁሉ ይቻላል አላቸው ። ፳፯

## ክፍል ፺፯ ፤ ጌታ ኢየሱስን የሚከተሉት ስለሚያገኙት ዋጋ ።

ጴጥሮስም እነሆ እንግዲህ እኛ ሁሉን ትተን ተከተልንህ ይለው ጀመር ። ፳፰

ጌታ ኢየሱስም መልሶ እንዲህ አላቸው ፤ ስለኔና ስለ ወንጌል ቤትን ፤ ወንድሞችን እኅቶችን ፤ አባትን ፤ እናትን ፤ ሚስትን ፤ እኅትን ልጅን እርሻን የሚተው ። ፳፱

በዚህ ዓለም በስደት በመቶ ዕጥፍ ቤትን እርሻን ወንድሞችን እኅቶችን አባትን እናትን ልጅን የማያገኝ የለም ፤ በሚመጣውም ዓለም የዘለዓለም ሕይወት ያገኛል ። ሮሜ ፲፯ ፲፱ ። ፴

ብዙዎች ፊተኞች ኋለኞችን ይሆናሉ ኋለኞችም ፊተኞችን ይሆናሉ ። ፴፩

## ክፍል ፺፰ ፤ ስለ ሕማሙና ስለ ሞቱ ።

በመንገድም ወደ ኢየሩሳሌም ሲወጡ ጌታ ኢየሱስ ቀድሟቸው ነበርና ደነገጡ የተከተሉትም ፈሩ ዐሥራ ሁለቱንም ወስዶ ይደርስበት ዘንድ ያለውን ይነግራቸው ጀመር ። ፴፪

እንግዲህ አላቸው እነሆ ወደ ኢየሩሳሌም እንወጣለን የካህናት አለቆችና ጻፎች የሰውን ልጅ ይይዙታል ይሙት በቃም ይፈርዱበታል ለአሕዛብም አሳልፈው ይሰጡታል ። ማቴ ፳ ፲፯ ፲፱ ። ሉቃ ፲፰ ፴፩ ፴፪ ። ፴፫

ያፌዙበታል ፤ ይተፉበታል ይገርፉታል ይገድሉታል በሦስተኛውም ቀን ይነሣል ። ፴፬

## ክፍል ፺፱ ፤ ስለ ዘብዴዎስ ልጆች ።

ሁለቱ የዘብዴዎስ ልጆች ያዕቆብና ዮሐንስ ከእሱ ጋር ሲሄዱ መምህር ! የለመንህን ልታደርግልን እንወዳለን ? አሉት ። ማቴ ፳ ፳ ፳፰ ። ፴፭

## ወንጌል ዘማርቆስ ፲ ።

፴፮ ወይቤሎሙ ምንተ ትፈቅዱ እግበር ለክሙ ።
፴፯ ወይቤልዎ ሀበነ ንንበር አሐድነ በየማንከ ወአሐድነ በጸጋምከ በውስተ ስብሐቲከ ።
፴፰ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ኢተአምሩ ዘትስእሉ ትክሉኑ እንከ ሰትየ ጽዋዕ ዘአነ እሰቲ ወጥምቀተ የኒ ዘአነ እጠመቅ ትጠመቁኑ ።
፴፱ ወይቤልዎ እወ ንክል ። ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ጽዋዕየሰ ዘአነ እሰቲ ትሰትዩ ወጥምቀትየኒ ዘአነ እጠመቅ ትጠመቁ ።
፵ ወነቢረሰ በየማንየ ወበጸጋምየ አኮ እነ ዘእሁበክሙ አላ ለከሐኢን እለ አስተዳለወ ሎሙ አቡየ ዘበሰማያት ።
፵፩ ወሰሚዖሙ ዐሠርቱ ተምዑ ዲበ ክልኤቱ አኀው ያዕቆብ ወዮሐንስ ።
፵፪ ወጸውዖሙ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ ኢተአምሩኑ ከመ መላእክቲሆሙ ለአሕዛብ ይኴንንዎሙ ወዐበይቶሙ ይቀንይዎሙ ።
፵፫ ወለክሙሰ አኮ ከማሁ አላ ዘይፈቅድ እምኔክሙ ይኩን ሊቀ ይኩንክሙ ገብረ ።
፵፬ ወዘይፈቅድ እምኔክሙ ይኩን ዐቢየ ይኩንክሙ ላእከ ።
፵፭ እስመ ወልደ እጓለ እመሕያውኒ ኢመጽአ ከመ ይትላእክዎ ዘእንበለ ዳእሙ ከመ ይትለአክ ወከመ ይቤዝዎሙ ለብዙኃን በነፍሱ ።

ክፍል ፵፱፤ በእንተ ጢሜዎስ ዕዉር ።

፵፮ ወበአ ኢያሪኮ ወወፂኦ እምህየ ወአርዳኢሁኒ ምስሌሁ ወሰብእኒ ብዙኃ ወሀሎ ጢሜዎስ ወልደ በርጢሜዎስ ዕዉር ይነብር ውስተ ፍኖት ወይስእል ።
፵፯ ወሰሚዖ ከመ ኢየሱስ ናዝራዊ ውእቱ ከልሐ ወይቤ ተመሃለኒ ኢየሱስ ወልደ ዳዊት ።
፵፰ ወገሠፅዎ ብዙኃን ከመ ያርምም ወአፈድፈደ ከሊሐ ወይቤ ወልደ ዳዊት ተማሃለኒ ።
፵፱ ወቆመ እግዚእ ኢየሱስ ወአዘዘ ይጸውዕዎ ለውእቱ ዕዉር ። ወጸውዕዎ ወይቤልዎ እመን ወተንሥእ ይጼውዐከ ሊቅ ።
፶ ወተንሥአ ወለበሰ ልብሶ ወመጽአ ኀበ እግዚእ ኢየሱስ ።
፶፩ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ ምንተ ትፈቅድ እግበር ለከ ። ወይቤሎ ውእቱ ዕዉር ረቢኒ ከመ እርአይ ።
፶፪ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ሑር ሃይማኖትከ አሕየወተከ ። ወርእየ ሶቤሃ ወተለዎ በፍኖት ።

## የማርቆስ ወንጌል ፲ ።

ምን ላደርግላችሁ ትወዳላችሁ? አላቸው ። ፴፮
በጌትነትህ አንዳችን በቀኝህ፥ አንዳችን በግራህ እንድንቀመጥ ፍቀድልን አሉት ። ፴፯
ጌታ ኢየሱስም እንዲህ አላቸው የምትለምኑትን አታውቁም፥ እኔ የምጠጣውን ጽዋ ልትጠጡ ትችላላችሁን? እኔ የምጠመቃትንስ ጥምቀት ትጠመቃላችሁን አላቸው ፤ ምዕ፥ ፲፬-፴፮ ። ሉቃ ፲፪፥፶ ። ፴፰
እምን እንችላለን አሉት፥ ጌታ ኢየሱስም እንዲህ አላቸው ፤ እኔ የምጠጣውን ጽዋስ ትጠጣላችሁ? እኔ የምጠመቃትንም ጥምቀት ትጠመቃላችሁ ። ግብ ሐዋ ፲፪፥፪ ። ፴፱
በቀኜና በግራዬ መቀመጥ ግን እኔ ለእናንተ የምሰጣችሁ አይደለም፥ በሰማያት ያለው አባቴ ላዘጋጀላቸው ነው እንጂ ። ፵
ዐሥሩም ሰምተው በሁለቱ ወንድማማቾች በያዕቆብና በዮሐንስ ተቈጡ ። ፵፩
ጌታ ኢየሱስም ጠርቶ እንዲህ አላቸው፥ አሕዛብን አለቆቻቸው እንደሚፈርዱባቸው ታላላቆቻቸውም እንደሚገዟቸው አታውቁምን? ፵፪
ለእናንተስ እንዲህ አይደለም፥ ከእናንተ አለቃ ሊሆን የሚወድ አገልጋይ ይሁናችሁ እንጂ ። ፵፫
ከእናንተ በላይ ሊሆን የሚወድም አገልጋይ ይሁናችሁ ። ምዕ ፱፥፴፭ ። ፵፬
የሰው ልጅም እኮ ሊያገለግልና ብዙዎችን ሊታደጋቸው እንጂ ሊያገለግሉት አልመጣም ። ፵፭

ክፍል ፵፱፥ ስለ ዕዉሩ ጢሜዎስ ።

ወደ ኢያሪኮም ገባ፥ ከዚያም በወጣ ጊዜ ደቀ መዛሙርቱ ከእርሱ ጋር ነበሩ ብዙ ሰውም ነበረ፥ የበርጢሜዎስ ልጅ ዕዉሩ ጢሜዎስም በመንገድ ተቀምጦ ይለምን ነበር ። ማቴ ፳፥፳፱-፴፬ ። ሉቃ ፲፰፥፴፭-፵፫ ። ፵፮
የናዝሬቱ ኢየሱስ በዚያ ሲያልፍ ሰምቶ የዳዊት ልጅ ኢየሱስ ሆይ! ማረኝ ብሎ ጮኸ ። ፵፯
ብዙዎች፥ ዝም እንዲል ገሠፁት፥ እርሱ ግን የዳዊት ልጅ ሆይ! ይቅር በለኝ እያለ ድምፁን ከፍ አድርጎ ጮኸ ። ፵፰
ጌታ ኢየሱስም ቆመና ያን ዕዉር እንዲጠሩት አዘዘ፥ እነርሱም ያንን ዕዉር መምህር ይጠራሃልና ተነሥ አትጠራጠር አሉት ። ፵፱
ተነሥቶም ልብሱን ለብሶ ወደ ጌታ ኢየሱስ መጣ ። ፶
ጌታ ኢየሱስም መልሶ ምን ላድርግልህ ትሻለህ? አለው፥ ያም ዕዉር መምህር! እንዳይ ነው አለው ። ፶፩
ጌታ ኢየሱስም ሂድ ሃይማኖትህ አዳነችህ አለው ። ወድያውም አየና በመንገድ ተከተለው ። ፶፪

ምዕራፍ ፲ወ፩፤

ክፍል ፺፤ በእንተ በአቱ ውስተ ኢየሩሳሌም ተፅዒኖ ዲበ ዕዋል ።

፩ ወአልጸቅዎ ኢየሩሳሌም ኀበ ቤተ ፋጌ ወቢታንያ እንተ ገበ ደብረ ዘይት ፈነወ ክልኤተ እምአርዳኢሁ ።

፪ ወይቤሎሙ ሑሩ ውስተ ሀገር እንተ ቅድሜክሙ ወበዊአክሙ ትረክቡ ዕዋለ እድግ እሡረ ዘኢተፅዕና ሰብእ ፍትሕዎ ወአምጽእዎ ሊተ ።

፫ ወእመቦ ዘይቤለክሙ ምንተ ትገብሩ በዝ እግዚኡ ይፈቅዶ፤ ወሰቤሃ ይፌንወክሙ ዝየ ።

፬ ወሖሩ ወረከቡ ዕዋለ እሡረ ኀበ አንቀጽ ውስተ ፍኖት ወፈትሕዎ ።

፭ ወይቤልዎሙ እለ ይቀውሙ ህየ ምንተ ትገብሩ ዘትፈትሑ ዕዋለ ።

፮ ወይቤልዎሙ በከመ አዘዞሙ እግዚእ ኢየሱስ ወኀደግዎሙ ።

፯ ወወሰድዎ ለዕዋል ኀበ እግዚእ ኢየሱስ ወረሐኑ ላዕሌሁ አልባሲሆሙ ወጼዐንዎ ።

፰ ወብዙኃን እለ ነጸፉ ቈጽለ መቲሮሙ እምዕፀው፤ ወቦ እለ ነጸፉ አልባሲሆሙ ውስተ ፍኖት ።

፱ እለሂ ይመርሑ፤ ወእለሂ ይተልዉ ይኬልሑ ወይብሉ "ሆሣዕና ቡሩክ ዘይመጽእ በስመ እግዚአብሔር„ ።

፲ ወቡርክት እንተ ትመጽእ መንግሥት በስመ እግዚአብሔር እንተ አቡነ ዳዊት ሆሣዕና በአርያም ።

፲፩ ወቦአ እግዚእ ኢየሱስ ኢየሩሳሌም ኀበ ቤተ መቅደስ ወርእየ ኵሎ ሰበ መስየ ሖረ ቢታንያ ምስለ ዐሠርቱ ወክልኤቱ ።

ክፍል ፺ወ፩፤ በእንተ በለስ ዘተረግመት ።

፲፪ ወበሳኒታ ወፂኦ እምቢታንያ ርኅበ ።

፲፫ ወርእየ በለስ እምርኁቅ ወባቲ ቈጽለ ወሖረ ይርአይ እመቦ ዘይረክብ ፍሬ በውስቴታ፤ ወበጺሖ ኀቤሃ አልቦ ዘረከበ ዘእንበለ ቈጽል ባሕቲቱ እስመ ኢኮነ ጊዜሁ ለበለስ ።

፲፬ ወአውሥአ ወይቤላ አልቦ ዘይበልዕ ፍሬ እምኔኪ ለዓለም፤ ወሰምዕዎ አርዳኢሁ ።

ክፍል ፺ወ፪፤ በእንተ እለ ያረኵሱ ቤተ መቅደስ ።

፲፭ ወበጺሖ ኢየሩሳሌም ቦአ ቤተ መቅደስ፤ ወአኀዘ ይስድድ እለ ይሠይጡ ወይሣየጡ በምኵራብ ወገፍትአ ማእዳቲሆሙ ለመወልጣን ወመናብርቲሆሙ ለእለ ይሠይጡ ርግበ ።

ምዕራፍ ፲፩፤

ክፍል ፺፤ በአህያ ላይ ተቀምጦ ወደ ኢየሩሳሌም ስለ መግባቱ ።

ኢየሩሳሌም ለመግባት ከደብረ ዘይት አጠገብ ቤተ ፋጌና ቢታንያ በደረሱ ጊዜ ከደቀ መዛሙርቱ ሁለቱን ላከ ። ሉቃ፡ ፲፱ ፳፱-፴፱ ። ዮሐ፡ ፲፪ ፲፪ - ፲፯ ። ፩

እንዲህም አላቸው በፊታችሁ ወዳለችው ሀገር ሂዱ በገባችሁም ጊዜ ሰው ያልተቀመጠበት የአህያ ግልገል ታሥሮ ታገኛላችሁ ፍቱና አምጡልኝ አላቸው። ፪

ምን ታደርጋላችሁ የሚላችሁ ቢኖር ጌታው ይሻዋል በሉትና ያን ጊዜ ወደዚህ ይሰዳችኋል ። ፫

ሂደውም በመንገድ አጠገብ ከበር ላይ የታሠረ አህያ አገኙና ፈቱት ። ፬

ከዚያ ቆመው የነበሩትም ምን ታደርጋላችሁ? አህያውን የምትፈቱት አሏቸው ። ፭

ጌታ ኢየሱስ እንደ አዘዛቸው ነገሯቸውና ተዉዋቸው ። ፮

ግልገሉን ወደ ጌታ ኢየሱስ ወሰደው ልብሳቸውን ደልድለው በዚያ ላይ አስቀመጡት ። ፯

ከዕንጨቶች ቅጠልን ዘንጥፈው ቈርጠው በመንገድ የጐዘጐዙ ብዙዎች ናቸው፤ ልብሳቸውንም ያነጠፉሉ ። ፰

በፊት የሚሄዱ፤ በኋላ የሚከተሉ እንዲህ እያሉ ይጮኹ ነበር፤ "ሆሣዕና በእግዚአብሔር ስም የሚመጣ የተባረከ ነው„ መዝ፡ ፻፲፰ ፳፭ ። ፱

በእግዚአብሔር ስም የምትመጣ ያባታችን ዳዊት መንግሥትም የተባረከች ናት፤ ሆሣዕና በአርያም እያሉ ። ፲

ጌታ ኢየሱስም ወደ ኢየሩሳሌም ቤተ መቅደስ ገባ፤ ሁሉንም አየና በመሸ ጊዜ ከዐሥራ ሁለቱ ጋር ወደ ቢታንያ ሄደ። ማቴ ፳፩ ፲፪—፳፪፡ ፲፱ ፵፭—፵፰ ። ፲፩

ክፍል ፺፩፤ ስለ ተረገመችው በለስ ።

በነጋውም ከቢታንያ በወጣ ጊዜ ተራበ ። ፲፪

በለስንም ከሩቅ ልየ ቅጠል ነበራት በውስጧ የሚያገኘው ፍሬ እንዳለ ሊያይ ሄደ ወደሷም በደረሰ ጊዜ ከቅጠል በቀር ያገኘው የለም፤ ጊዜው የበለስ አልነበረምና ። ፲፫

ጌታም መልሶ ለዘለዓለም ከንቺ የሚበላ ፍሬ አይኑር አላት፤ ደቀ መዛሙርቱም ሰሙ ። ፲፬

ክፍል ፺፪፤ ቤተ መቅደስን ስለሚያረክሱ ።

ኢየሩሳሌም በደረሰም ጊዜ ወደ ቤተ መቅደስ ገብቶ በምኵራቡ የሚሸጡትንና የሚገዙትን ያባርራቸው ጀመር፤ የለዋጮዎችንም መደብርና ርግብ የሚሸጡትን ወንበሮች ገለበጠ ። ፲፭

፲፮ ወከልአ ከመ አልቦ ዘያኀልፍ ንዋየ እንተ ምኵራብ።

፲፯ ወመሀሮሙ ወይቤሎሙ አኮኑ ጽሑፍ ዘይብል
ቤትየሰ ቤተ ጸሎት ይኩን ለኵሉ አሕዛብ፤ ወአንት
ሙሰ ረሰይክምዎ በዓተ ፈያት ወሰረቅት ።

፲፰ ወሰምዑ ሊቃነ ካህናት ወጸሐፍት ወኀሠሡ እንተ
ኀበ ይቀትልዎ ወፈርህዎ እስመ ኵሉ ሕዝብ ያነክሩ
ምሕርቶ ።

፲፱ ወሶበ መስየ ወፅአ አፍአ እምሀገር ።

፳ ወበጊብአቶሙ በነግህ ረከብዋ ለይእቲ በለስ ይብ
ስተ እምሥርዋ ።

፳፩ ወተዘከረ ጴጥሮስ ወይቤሎ ሊቅ ነያ እንታክቲ በለስ
እንተ ረገምካ የብሰት ።

፳፪ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ ይኩን
ውስቴትክሙ ሃይማኖተ እግዚአብሔር ።

፳፫ አማን እብለክሙ ለእመ ትብልዎ ለዝንቱ ደብር
ተንሥእ ወተወረው ውስተ ባሕር ወኢይናፍቅሙ
በልብክሙ ወተአመንክሙ ከመ ዘነበብክሙ ይከ
ውን ወትረክቡ ።

፳፬ ወበእንተ ዝንቱ እብለክሙ ኵሉ ዘጸለይክሙ ወሰ
አልክሙ እንዘ ትትአመኑ ከመ ትረክቡ ወይከውን
ለክሙ ።

፳፭ ወሶበሂ ትጼልዩ ኅድጉ ለቢጽክሙ ዘተሐየስክም
ዎሙ ከመ ይኅድግ ለክሙ አቡክሙ ዘበሰማያት
አበሳክሙ ።

፳፮ ወእመሰ አንትሙ ኢኀደግሙ አቡክሙኒ ሰማያዊ
ኢየኀድግ ለክሙ አበሳክሙ ።

ክፍል ፶ወ፫ ፤ በእንተ ተስእሎተ መበሕት ።

፳፯ ወሖረ ካዕበ ኢየሩሳሌም ወእንዘ ያንሶሱ በምኵራብ
መጽኡ ኀቤሁ ሊቃነ ካህናት ወጸሐፍት ወረበናት ።

፳፰ ወይቤልዎ በመበሕት መኑ ትገብር ዘንተ፤ ወመኑ
አብሐከ ትግበር ዘንተ ።

፳፱ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ እነሂ እሴአለክሙ
አሐተ ነገረ ወንግሩኒ፤ ወእነሂ እነግረክሙ በመበ
ሕተ መኑ እገብር ከመዝ ።

፴ ጥምቀቱ ለዮሐንስ እምአይቴኑ እምሰማይኑ አው
እምሰብእ አይድዑኒ ።

፴፩ ወተባሀሉ በበይናቲሆሙ ለእመ ንቤ እምሰማይ
ይብለነ ለምንት ኢአመንክምዎ ።

፴፪ ወእመ ንብል እምሰብእ ንፈርሆሙ ለሕዝብ እስመ
ኵሎሙ ከመ ነቢየ ይሬእይዎ ለዮሐንስ ።

፴፫ ወተሠጥውዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ወይቤልዎ ኢነአ
ምር፤ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ እነኒ
ኢይነግረክሙ በመበሕተ መኑ እገብር ከመዝ ።



በምኵራብም በኩል ገንዘብን የሚያስተላልፍ እንዳ ፲፮
ይኖር ከለከለ ።
እንዲህ ብሎም አስተማራቸው ፤ ቤቴ ለአሕዛብ ሁሉ ፲፯
"የጸሎት ቤት ይሁን" የሚል ተጽፎ የለምን እናንተ
ግን የሌቦችና የቀማኞች ዋሻ አደረጋችሁት ። ኢሳ
፶፮ ፣ ፯ ። ኤር ፯ ፣ ፲፩ ።
የካህናት አለቆችና ጻፎች ሰምተው የሚገድሉበትን ፲፰
ፈለጉ ፤ ግን ፈሩት ፤ ሕዝቡ ሁሉ ትምህርቱን ያደንቁ
ነበርና ።
በመሸም ጊዜ ከከተማ ወደ ውጭ ወጣ ። ፲፱
በነጋውም ተመልሰው ያችን በለስ ከሥሯ ደርቃ ፳
አገኟት ። ቍ ፲፬ ።
ጴጥሮስም አስታውሶ መምህር፤ እነሆ ያቺ የረገም ፳፩
ካት በለስ ደርቃለች አለው ። ዕብ ፯ ፣ ፰ ።
ጌታ ኢየሱስም መልሶ እንዲህ አላቸው ፤ የእግዚአብ ፳፪
ሔርን ማመን በእናንተ ይኑር ። ዮሐ ፲፬ ፣ ፩ ።
እውነት እላችኋለሁ ይህን ተራራ ተነሥተህ ወደ ፳፫
ባሕር ተወርወር ብትሉት በልቡናችሁ በትጠራጠ
ሩና ብታምኑ እንደ ተናገራችሁት ሆኖ ታገኙላ
ችሁ ። ማቴ ፲፯ ፣ ፳ ።
ስለዚህም አምናችሁ የለመናችሁትን ሁሉ እንደ ፳፬
ሚሆንላችሁም እነግራችኋለሁ ። ማቴ ፯ ፣ ፯ ። ዮሐ
፲፬ ፣ ፲፫ ።
በምትጸልዩበትም ጊዜ ወንድሞቻችሁን የነቀፉችሁ ፳፭
በቸውን ተዉ ፤ ሰማያዊ አባታችሁም በደላችሁን
ይቅር እንዲላችሁ ። ማቴ ፮ ፣ ፳፫ ።
እናንተ ይቅር ካላላችሁ ሰማያዊ አባታችሁም ይቅር ፳፮
አይላችሁም ። ማቴ ፮ ፣ ፲፬ - ፲፭ ።

ክፍል ፶፫ ፡ ስለ ክሃሊነቱ የቀረበ ጥያቄ ።

ዳግመኛም ወደ ኢየሩሳሌም ሄደ በምኵራብም ሲመ ፳፯
ላለስ የካህናት አለቆች ሽማግሎችና ጻፎች ወደርሱ
መጡ ። ማቴ ፳፩ ፣ ፳፫ - ፳፯ ። ሉቃ ፳ ፣ ፩ - ፰ ።
በማን ሥልጣን ይህን ታደርጋለህ? ይህንስ ታደርግ ፳፰
ዘንድ ሥልጣን ማን ሰጠህ? አሉት ።
ጌታ ኢየሱስም አላቸው ፤ እኔም አንድ ነገር እጠይ ፳፱
ቃችኋለሁና ንገሩኝ ፤ እኔም በማን ሥልጣን እንዲህ
እንደማደርግ እነግራችኋለሁ አላቸው ።
የዮሐንስ ጥምቀት ከወዴት ነው? ከእግዚአብሔር ፴
ነው ወይስ ከሰው? መልሱልኝ ።
እርስ በርሳቸው እንዲህ ተባባሉ ከሰማይ ነው ብን ፴፩
ለው ለምን አላመናችሁበትም ይለናል ።
ከሰው ነው ብንለውም ሕዝቡን እንፈራለን ፤ ሁሉም ፴፪
ዮሐንስን እንደ ነቢይ ያዩት ነበርና ።
መልሰውም ጌታ ኢየሱስን አናውቅም አሉት ፤ ጌታ ፴፫
ኢየሱስም መልሶ እኔም ይህን በማን ሥልጣን እንደ
ማደርግ አልነግራችሁም አላቸው ።

## ምዕራፍ ፲ወ፪ ፤

### ክፍል ፶ወ፬ ፡ ምሳሌ በእንተ ዓጸደ ወይን ወዓቀብቱ ።

፩ ወአኀዘ ይመስል ሎሙ ወይቤሎሙ ብእሲ ተከለ
ወይነ ወዐጠና ወአክረየ ምክያደ ወሐነፀ ማኅፈደ
ውሉቴቱ ወሚመ ሎቱ ገበረ ወዐቀብተ ወይን ወነገደ።
፪ ወፈነወ ገብሮ ኀበ ዐቀብተ ወይን በጊዜሁ ያምጽእ
ሎቱ እምፍሬ ወይኑ ።
፫ ወአኀዝዎ ወቀሠፍዎ ወፈነውዎ ዕራቆ ።
፬ ወካዕበ ፈነወ ኀቤሆሙ ካልአ ገብሮ ፤ ወኪያሁኒ ወገ
ርዎ ወኰርዕዎ ወፈነውዎ አኅሚሮሙ ።
፭ ወፈነወ ሣልሰ ገብሮ ወኪያሁኒ ቀተልዎ ፤ ወፈነወ
ካልአነ አግብርተ ብዙኃነ ፤ በ ዘቀሠፉ ፤ ወበ ዘቀተሉ ፤
፮ ወቦቱ አሐዱ ወልድ ዘያፈቅር ፤ ወፈነዎ ኀቤሆሙ
ድኅረ ኵሉ እንዘ ይብል የኀፍርዎ ለወልድየሰ ።
፯ ወሰበ ርእይዎ ዓቀብት ይቤሉ ዝንቱ ውእቱ ወራ
ሲሁ ንዑ ንቅትሎ ወንርከብ ርስቶ ።
፰ ወአኀዝዎ ወአውጽእዎ አፍአ እምዓፀደ ወይን ወቀ
ተልዎ ።
፱ ምንተ እንከ ይሬስዮሙ በዓለ ወይን ይመጽእ ወይ
ቀትሎሙ ለእልክቱ ገባር ወይሁብ ወይኖ ለካልአን።
፲ ወዘኒ ኢያንበብክሙኑ ውስተ መጽሐፍ እብን እንተ
መነንዋ ነደቅት ይእቲ ኮነት ውስተ ርእሰ ማዕዘንት ።
፲፩ እምኀበ እግዚአብሔር ኮነት ዛቲ ፤ ወነክር ይእቲ ለአ
ዕይንቲነ ።
፲፪ ወፈቀዱ የአኀዝዎ ወፈርህዎሙ ለሕዝብ እስመ አእ
መሩ ከመ በእንቲአሆሙ ይቤ ዘንተ አምሳለ ፤ ወኀ
ደግዎ ወሖሩ ።

### ክፍል ፶ወ፭ ፡ በእንተ ተሰብሎተ ዲናር ።

፲፫ ወፈነዉ ኀቤሁ ፈሪሳውያን ምስለ ሰብአ ሄሮድስ
ከመ ያዕሕትዎ በቃሉ ።
፲፬ ወመጽኡ ኀቤሁ ወይቤልዎ ሊቅ ነአምር ከመ ጻድቅ
አንተ ወኢያኀዝነከ መኑሂ ወኢታደሉ ለገጸ ሰብእ
ወበጽድቅ ትሜህር ፍኖተ እግዚአብሔር ይከውነነሁ
ነሀብ ጸባሕተ ዲናር ለነጋሢ አው አልቦ ።
፲፭ ወአእመሮሙ እግዚእ ኢየሱስ ጕሕሉቶሙ ወይቤ
ሎሙ ለምንት ታሜክሩኒ ወአምጽኡ ዲናረ ወእር
እዩኒ ።
፲፮ ወአምጽኡ ሎቱ ወይቤሎሙ ዘመኑ ዝንቱ መልክዑ
ወመጽሐፉ ፤ ወይቤልዎ ዘነጋሢ ።

## ምዕራፍ ፲፪ ።

### ክፍል ፶፬ ፡ ስለ ወይኑ ቦታና ስለ ጠባቆቹ ።

ምሳሌም ይመስልላቸው ጀመረ እንዲህም አላቸው ፤ ፩
አንድ ሰው ወይን ተክሎ አጠረው ፤ መጥመቂያን
አስቈፈረለት በውስጡም ግንብ ሠራ ፤ ሠራተኞችንና
ተክል ጠባቆችን ሾሞለት ሄደ ። ኢሳ ፭ ፩–፲ ።
ማቴ ፳፩ ፴፫ ፵፮ ። ሉቃ ፳ ፱–፲፱ ። ኤር ፪ ፳፩ ።
ከወይኑ ፍሬ ያመጣለት ዘንድ በጊዜው ወደ ወይን ፪
ጠባቆች አገልጋዩን ላከ ።
ይዘውም ገርፈው ባዶ እጁን ሰደዱት ። ፫
ዳግመኛም ሌላውን አገልጋይ ወደርሱ ላከ እርሱንም ፬
ደብድበው ቀጥቅጠው አዋርደው ሰደዱት ።
ሦስተኛውንም አገልጋዩን ላከ ፤ እርሱንም ገደሉት ፤ ፭
ሌሎች ብዙ አገልጋዮችንም ሰደደና ከነርሱም የገረ
ፉት አሉ ፤ የገደሉትም አሉ ።
የሚወደው አንድ ልጅም ነበረውና ከሁሉ በኋላ ፮
ልጄንስ ያፍሩታል ብሎ ወደነርሱ ላከ ።
ጠባቆችም በዩት ጊዜ ወራሹ ይህ ነው ኑ እንግደለ ፯
ውና ርስቱን እጅ እናድርግ አሉ ።
ይዘው ከወይኑ ቦታ ወደ ውጭ አውጥተው ገደ ፰
ሉት ። ዕብ ፲፫ ፲፪ ።
እንግዲህ የወይኑ ባለቤት ምን ያደርጋቸው ይሆን ? ፱
መጥቶ እነዚያን ጠባቂዎች ያጠፋቸዋል ወይኑንም
ለሌሎች ይሰጣል ።
ይህንስ በመጽሐፍ አላነበባችሁምን አናጢዎች የና ፲
ቋት ደንጊያ እርሷ የማዕዘን ራስ ላይ ሆነች ። መዝ
፻፲፰ ፳፪ ፳፫ ። ማቴ ፳፩ ፵፪ ። ግብ ሐዋ ፬ ፲፩ ።
እርሷ ከእግዚአብሔር ዘንድ ሆነች ለዓይኖቻችንም ፲፩
ድንቅ ናት ።
ሊይዙትም ወደዱ ነገር ግን ሕዝቡን ፈሩ ይህን ፲፪
ምሳሌ ስለ እነሱ እንደ ተናገረ አውቀዋልና ትተዉ
ትም ሄዱ ።

### ክፍል ፶፭ ፡ ስለ ዲናር የቀረበ ጥያቄ ።

ፈሪሳውያንም በቃሉ ያስቱት ዘንድ ከሄሮድስ ሰዎች ፲፫
ጋር ሰው ወደርሱ ላኩ ። ምዕ ፫ ፯ ። ማቴ ፳፪ ።
፲፭ ፳፪ ። ሉቃ ፳ ፳–፳፯ ።
እነሱም መጥተው እንዲህ አሉት ፤ መምህር አንተ ፲፬
እውነተኛ እንደሆንክ እናውቃለን ማንም ማን እያ
ሳዝንህም በእውነት የእግዚአብሔር መንገድ ታስተ
ምራለህ እንጂ ለሰው ፊት አታደላም ፤ ለንጉሥ
ግብር መስጠት ይገባልን ወይስ አይገባም ?
ጌታ ኢየሱስም ተንኰላቸውን በወቀና ለምን ትፈ ፲፭
ትኑኛላችሁ ? ገንዘቡን አምጥታችሁ አሳዩኝ አላቸው ።
እነሱም አመጡለት ይህ መልኩ ጽሕፈቱስ የማን ፲፮
ነው ? አላቸው የንጉሥ ነው አሉት ።

፲፯ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ ሀቡ ዘን
ጋሢ ለንጉሢ ፤ ወዘእግዚአብሔርኒ ግበሩ ለእግዚአብ
ሔር ፤ ወአንከርዎ ።

ክፍል ፱ወ፮ ፤ በእንተ እለ ይብሉ
አልቦ ትንሣኤ ሙታን ።

፲፰ ወመጽኡ ኀቤሁ ሰዱቃውያን እለ ይብሉ አልቦ ትን
ሣኤ ሙታን ፤ ወተስእልዎ ወይቤልዎ ።
፲፱ ወተስእልዎ ወይቤልዎ ሊቅ ሙሴ ጸሐፈ ለነ እንዘ
ይብል ለእመበ ዘሞተ እኁሁ ወኀደገ ብእሲቶ ወአ
ልቦቱ ውሉድ ፤ ያውስባ እኁሁ ለብእሲቱ ወያቅም
ዘርአ ለእኁሁ ።
፳ ወሀለዉ እንከ በኀቤነ ሰብዐቱ አኃው ወአውሰበ
ዘይልህቅ ብእሲተ ወሞተ እንዘ አልቦ ውሉድ ።
፳፩ ወአውሰባ ካልኡኒ ወሞተ እንዘ አልቦ ውሉድ ፤
ወሣልሶኒ ከማሁ ።
፳፪ ወሰብዐቲሆሙ አውሰብዋ ወኢኀደጉ ውሉደ ፤ ወድ
ኅረ ኵሎሙ ሞተት ይእቲ ብእሲት ።
፳፫ እመ የሐይዉ ሙታን ለመኑ እምኔሆሙ ትከውና
ብእሲተ ፤ እስመ ሰብዐቲሆሙ አውሰብዋ ።
፳፬ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ ስሕትክሙ
ዘኢያእመርክሙ መጻሕፍተ ወኢኃይለ እግዚአብሔር ።
፳፭ ወአመሰ የሐይዉ ምውታን ኢያወስቡ ወኢይትዋ
ሰቡ ፤ አላ ከመ መላእክተ እግዚአብሔር እሙንቱ
በሰማያት ።
፳፮ ወከመሰ የሐይዉ ምውታን ኢያንበብክሙኑ በው
ስተ መጽሐፈ ሙሴ ዘይቤሎ እግዚአብሔር በኀበ
ዕፀ ጳጦስ እንዘ ይብል ፤ አነ ውእቱ እግዚአብሔር
አምላክከ ፤ አምላከ አብርሃም ፤ ወአምላከ ይስሐቅ
ወአምላከ ያዕቆብ ።
፳፯ ኢኮነ አምላከ ሙታን ፤ አላ አምላከ ሕያዋን
ውእቱ ፤ ወአንትሙሰ ብዙኀ ተጌግዩ ።

ክፍል ፱ወ፯ ፤ ተስእሎ እምኀበ አሐዱ ጸሐፊ ።

፳፰ ወመጽአ አሐዱ ጸሐፊ ሰሚዖ ከመ ተኃሠሥዎ
ወሰበ ርእየ ከመ ሠናየ ተሰጥዎሙ ፤ ተስእሎ ወይ
ቤሎ አይኑ ትእዛዝ ቀዳሚት እምኵሉ ።
፳፱ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ ዛቲ ይእቲ
ቀዳሚት እምኵሉ ትእዛዝ ስማዕ እስራኤል ፤ አሐዱ
ውእቱ እግዚአብሔር አምላክከ ።
፴ ወአፍቅሮ ለእግዚአብሔር አምላክከ በኵሉ ልብከ
ወበኵሉ ነፍስከ ፤ ወበኵሉ ሕሊናከ ፤ ወበኵሉ ኃይ
ልከ ፤ ዛቲ ይእቲ ቀዳሚት ትእዛዝ ።
፴፩ ወከልእታሂ እንተ ትመስላ ፤ ዛቲ ይእቲ አፍቅር ቢጸከ
ከመ ነፍስከ ፤ ወዘየዓቢ እምእላንቱ ትእዛዛት አልቦ ።



ጌታ ኢየሱስም መልሶ የንጉሥን ለንጉሥ ስጡ ፤ ፲፯
የእግዚአብሔርንም ለእግዚአብሔር አድርጉ አላ
ቸው ፤ አደነቁት ። ሮሜ ፲፫ ፣ ፯ ።

ክፍል ፺፮ ፤ ትንሣኤ ሙታን የለም
ስለሚሉ ወገኖች ።

ትንሣኤ ሙታን የለም የሚሉ ሰዱቃውያንም ወደ ፲፰
ርሱ መጡ ። ማቴ ፳፪ ፣ ፳፫ - ፴፫ ሉቃ ፳ ፣ ፳፯ - ፵ ።
እንዲህ ብለውም ጠየቁት ፤ መምህር! ወንድሙ ፲፱
ሚስቱን ትቶ የሞተበት ሰው ቢኖር ልጅም ባይኖ
ረው ወንድሙ ሚስቱን አግብቶ ለወንድሙ ዘር
ይተክ ብሎ ሙሴ ጽፎልናል ። ዘዳ ፳፭ ፣ ፭ ።
እንግዲህ በእኛ ዘንድ ሰባት ወንድማማቾች ነበሩ ፤ ፳
ታላቁ ሚስት አግብቶ ልጅ ሳይወልድ ሞተ ።
ሁለተኛውም አገባትና ልጅ ሳይወልድ ሞተ ፤ ሦስተ ፳፩
ኛውም እንዲሁ ።
ሰባቱም አገቡዋት ዘርም አልተዉም ፤ ከሁሉም በኋላ ፳፪
ያቺ ሴት ሞተች ።
እንግዲህ ሙታን በሚነሡበት ጊዜ ከነሱ ለማንኛውም ፳፫
ሚስት ትሆናለች? ሰባቱም አግብተዋታልና ።
ጌታ ኢየሱስም መልሶ እንዲህ አላቸው ፤ መጻሕፍት ፳፬
ንና የእግዚአብሔርን ኃይል ባለማወቅ ትሳሳታችሁ ።
ሙታንስ በተነሡ ጊዜ አያገቡም አይጋቡም ፤ እነሱ በሰ ፳፭
ማያት እንደ እግዚአብሔር መላእክት ናቸው እንጂ ።

ሙታን እንዲነሡማ እግዚአብሔር በዕፀ ጳጦስ ዘንድ ፳፮
ያንተ አምላክ ፤ የአብርሃም አምላክ ፤ የይስሐቅ አም
ላክ ፤ የያዕቆብ አምላክ ፤ እኔ እግዚአብሔር ነኝ ብሎ
የነገረውን በሙሴ መጽሐፍ አላነበባችሁምን? ዘፀ
፫ ፣ ፮ - ፯ ።
እንግዲያውስ የሕያዋን አምላክ ነው እንጂ ፤ የሙ ፳፯
ታን አምላክ አይደለም ፤ እናንተ ግን በብዙ ትሳሳ
ታላችሁ ።

ክፍል ፺፯ ፤ ከአንድ ጸሐፊ የቀረበ ጥያቄ ።

እንደ ተከራከሩትም ሰምቶ አንድ ጸሐፊ መጣና ፳፰
በሚገባ እንደ መለሰላቸው ባየ ጊዜ ፤ ከሁሉ የምትበ
ልጠዋ ትእዛዝ የትኛዪቱ ናት? ብሎ ጠየቀው ።
ማቴ ፳፪ ፣ ፴፬ - ፵ ። ሉቃ ፲ ፣ ፳፭ - ፳፰ ።
ጌታ ኢየሱስም መልሶ እንዲህ አለው ፤ ከትእዛዝ ፳፱
ሁሉ የምትበልጠው ይህች ናት ፤ "እስራኤል ሆይ!
ስማ አምላክህ አንድ እግዚአብሔር ነው" ። ዘዳ ፮፡፬።
"እግዚአብሔር አምላክህን በፍጹም ልብህ ፤ በፍጹም ፴
ሰውነትህ ፤ በፍጹም አሳብህ ፤ በሚቻልህ ሁሉ ውደ
ደው" ፤ አንደኛዪቱ ትእዛዝ ይህች ናት ።
የምትመስላት ሁለተኛዪቱም ይህች ናት ፤ "ወንድም ፴፩
ህን እንደ ራስህ ውደድ" ፤ ከእነዚህ ትእዛዛት የሚበ
ልጥ የለም ። ዘሌ ፲፱ ፣ ፲፰ ።

፴፪ ወይቤሎ ውእቱ ጸሐፊ ሠናየ ትቤ ሊቅ፤ አማን አሐዱ
ውእቱ እግዚአብሔር ወአልቦ ባዕድ ዘእንበሌሁ ።

፴፫ ወከመ ታፍቅር በኵሉ ልብከ፤ ወበኵሉ ነፍስከ፤ ወበ
ኵሉ ሕሊናከ፤ ወበኵሉ ኃይልከ፤ ወከመ ታፍቅር
ቢጸከ ከመ ነፍስከ ፤ ወዝንቱ ይኄይስ እምኵሉ
መባእ ወእምኵሉ መሥዋዕት ።

፴፬ ወርእዮ ከመ ጠቢብ ውእቱ፤ ይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ
ኢኮንከ ርኁቀ እመንግሥተ እግዚአብሔር ወአልቦ
እንከ ዘተኀበለ ይሰአሎ ።

ክፍል ፺ወ፰፤ ተስእሎ እምኀበ
መድኃን ለፈሪሳውያን ።

፴፭ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ እንዘ ይሜህሮሙ በም
ኵራብ እፎ ይብሉ ጸሐፍት ከመ ክርስቶስ ወልደ
ዳዊት ውእቱ ።

፴፮ ወለሊሁ ዳዊት ይቤ በመንፈስ ቅዱስ፤ ይቤሎ እግ
ዚእ ለእግዚእየ ንበር በየማንየ እስከ እገብኦሙ ለጸ
ላእትከ ታሕተ መከየደ እገሪከ ።

፴፯ ዘለሊሁ እንከ ዳዊት እግዚእየ ይቤሎ፤ እፎ እንከ
ይከውኖ ወልዶ፤ ወኵሉ ሕዝብ ሠናየ ያጸምዕዎ ።

ክፍል ፺ወ፱፤ በእንተ ተዐቅቦተ ግብር እምጸሐፍት ።

፴፰ ወይቤሎሙ እንዘ ይሜህሮሙ ፤ ዑቁ ወተዐቀቡ
እምጸሐፍት እለ ይፈቅዱ ያንሶስዉ ተላቢሶሙ ወይ
ትአምኁዎሙ በምሥያጣት ።

፴፱ ወያፈቅሩ ነቢረ ፍጽም በውስተ አዕዋዳት፤ ወርእሰ
ምርፋቃት በውስተ ምሳሐት ።

፵ እለ ይውኅጥዎን ለአብያተ መበለታት ወይትሜየኑ
በነዊኅ ጸሎቶሙ፤ እሉ ይረክቡ ዘየዐቢ ኵነኔ ።

ክፍል ፻፤ በእንተ ክልኤ ጸሪቅ ።

፵፩ ወነቢሮ እግዚእ ኢየሱስ ኆኅተ ምኵራብ መንጸረ
ሙዳየ ምጽዋት ይሬኢ ሰብአ ዘያበውኡ ጸሪቀ
ወይወድዩ ውስተ ሙዳየ ምጽዋት፤ ወብዙኃን አብዕ
ልት እለ አብኡ ብዙኀ ።

፵፪ ወመጽአት አሐቲ ብእሲት ነዳይት መበለት፤ ወአብ
አት ክልኤ ጸሪቀ ዘየአክሉ ቈንደራጤስ ።

፵፫ ወጸውዖሙ ለአርዳኢሁ ወይቤሎሙ፤ አማን እብለ
ክሙ ከመ ዛቲ ነዳይት መበለት አብዝኀት አብአ
እምኵሎሙ እለ አብኡ ውስተ ሙዳየ ምጽዋት ።

ያም ጸሐፊ እንዲህ አለው፤ መምህር፤ መልካም ብለ ፴፪
ሃል እግዚአብሔር በእውነት አንድ ነው ከርሱም
በቀር ሌላ የለም ።
በፍጹም ልብህ በፍጹም ሰውነትህ፤ በፍጹም አሳ ፴፫
ብህ በሚቻልህ ሁሉ እንድትወደው መሆን ነው
ወንድምህንም እንደ ራስህ እንድትወድ መሆን ነው
ይህም ከመሥዋዕት ሁሉ ይበልጣል። ፩ ሳሙ ፲፭ ፳፪፤
ብልህ እንደሆነም አይቶ ጌታ ኢየሱስ ከእግዚአብ ፴፬
ሔር መንግሥት የራቅህ አይደለህም አለው፤ ከዚህ
በኋላ ሊጠይቀው የደፈረ የለም ። ግብ ሐዋ ፳፮
፳፯—፳፱ ።

ክፍል ፺፰፤ ከመድኃን
ለፈሪሳውያን የቀረበ ጥያቄ ።

ጌታ ኢየሱስም እንዲህ አላቸው በምኵራብ ሲያስተ ፴፭
ምራቸው ጸሐፎች ክርስቶስ እንዴት የዳዊት ልጅ ነው
ይላሉ? ማቴ ፳፪ ፵፩—፵፮ ። ሉቃ ፳ ፵፩—፵፬ ።
እርሱ ራሱ ዳዊት በመንፈስ ቅዱስ ጌታ ጌታዬ ፴፮
ጠላቶችህን ከእግርህ ጫማ በታች እስከገዛቸው
ድረስ በቀኜ ተቀመጥ አለው አለሳ? መዝ ፻፲ ፩ ።
እንግዲህ እርሱ ራሱ ዳዊት ጌታዬ ያለው እንዴት ፴፯
ልጁ ይሆነዋል? ሕዝቡም ሁሉ ደስ ብሏቸው ያዳም
ጡት ነበር ።

ክፍል ፺፱፤ ከጸሐፎች ግብር ስለ መጠበቅ ።

ሲያስተምራቸውም እንዲህ አላቸው፤ ዐውቁ ረዣ ፴፰
ዥም ልብስ ለብሰው ወዲያ ወዲህ ማለትን በገበ
ያም እጅ ሊነሡዋቸው ከሚወዱ ከጸሐፎች ተጠበቁ ።
ማቴ ፳፫ ፩—፴፮ ። ሉቃ ፳ ፵፭—፵፯ ።
በአደባባዮችም ፊት ለፊት መቀመጥን በማእድም ፴፱
ጊዜ በራስነት መቀመጥን ይወዳሉ ።
በረዥም ጸሎታቸው አመካኝተው የመበለቶችን ፵
ቤቶች (ገንዘብ) የሚውጡ እሊህ ጽኑ ፍርድ ይቀ
በላሉ ።

ክፍል ፻፤ ስለ ሁለት መሐለቅ ።

ጌታ ኢየሱስም ከምኵራቡ ደጅ በሙዳየ ምጽዋት ፵፩
ፊት ለፊት ተቀምጦ ገንዘብ የሚያገቡ በሙዳየ ምጽ
ዋቱ የሚጨምሩ ሰዎችን ያይ ነበር፤ ብዙ ገንዘብ
ያገቡ ባለጸጎችም ብዙዎች ነበሩ ። ፪ ነገ ፲፪ ፱ ።
ሉቃ ፳፩ ፩—፬ ።
አንዲት ድኻ ሴት መጥታ ድሪም የሚያህሉ ሁለት ፵፪
ገንዘቦች አገባች ።
ደቀ መዛሙርቱንም ጠርቶ እንዲህ አላቸው፤ በሙ ፵፫
ዳየ ምጽዋቱ ገንዘብ ካገቡት ሁሉ ይህች ድኻ ሴት
አብዝታ እንዳገባች በእውነት እላችኋለሁ ።

፴፬ እስመ ኵሎሙ እለ አብኡ እምተረፈሙ አብኡ ፤
ወይእቲሰ እምተፅናሳ ኵሎ ዘቦቱ ሴሲተ ወኵሎ
መንበርታ ።

ምዕራፍ ፲ወ፫ ፤

ክፍል ፷ወ፩ በእንተ ንፅተተ

ቤተ መቅደስ ወኢየሩሳሌም ።

፩ ወወፂኦ እምኵራብ ይቤሎ አሐዱ እምአርዳኢሁ
ሊቅ ርኢ ምንተ ይመስል ንድቁ ወአበኒሁ ።

፪ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ ፤ ትሬኢኑ
ዘንተ ኵሎ ንድቀ ዐቢየ ኢይትኀደግ ዝየ እብን
ዲበ እብን ዘኢይትነሠት ።

፫ ወእንዘ ይነብር እግዚእነ ውስተ ደብረ ዘይት አንፃረ
ምኵራብ ተስእልዎ በባሕቲቶሙ ጴጥሮስ ፤ ወያዕ
ቆብ ፤ ወዮሐንስ ፤ ወእንድርያስ ።

፬ ወይቤልዎ ንግረነ ማእዜ ይከውን ዝንቱ ወምንት
ትእምርቱ አመ ይከውን ዝንቱ ኵሉ ።

፭ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወአኀዘ ይበሎሙ ዑቁ
ኢያስሕቱክሙ ።

፮ እስመ ብዙኃን ይመጽኡ በስምየ እንዘ ይብሉ አነ
ውእቱ ክርስቶስ ፤ ወያስሕትዎሙ ለብዙኃን ።

፯ ወአመ ሰማዕክሙ አፅባዐ ወድምፀ ፀባኢት ኢት
ደንግፁ እስመ ሀለዎ ይኩን ዝንቱ ፤ ወባሕቱ አኮ
ሰቤሃ ዘየኃልቅ ።

፰ ወይትነሣእ ሕዝብ ዲበ ሕዝብ ወነገሥት ዲበ ነገሥት
ወይከውን ድልቅልቅ በበብሔሩ ወይመጽእ ረኃብ ።

፱ ወዝንቱ ቀዳሚሁ ለፃዕር ፤ ወአንትሙሰ ዑቁ ርእሰ
ክሙ ወይወስዱክሙ አዕዋዳተ ወይቀሥፉክሙ
በመኳርብት ወይትበጽሑክሙ ኀበ መላእክት ወነገ
ሥት በእንቲአየ ፤ ከመ ይኩን ስምዐ ላዕሌሆሙ ።

፲ ወለኵሎሙ አሕዛብ ይደሉ ይቅድሙ ወይስብክዎ
ለወንጌል ።

፲፩ ወሶበ ያበጽሑክሙ ኢትቅድሙ ተሐልዩ ወዘትነ
ብቡ ወዘአንበብክሙ ሰቤሃ ንቡ እስመ ኢኮንክሙ
አንትሙ ዘትነብቡ ዘእንበለ መንፈስ ቅዱስ ።

፲፪ ወያገብእ እኁ እኅዋሁ ለሞት ፤ ወአብ ወልዶ ፤
ወውሉድ ይትነሥኡ ዲበ አዝማዲሆሙ ወይቀትል
ዎሙ ።

፲፫ ወትከውኑ ጽሉአነ በኀበ ኵሉ ሰብእ በእንተ ስምየ ፤
ወዘሰ አዝለፈ ትዕግሥቶ ውእቱ ይድኅን ።

፲፬ ወሶበ ርኢክሙ ኀሣሮ ለሙስና ዘይቤ ዳንኤል ነቢይ
ዘይቀውም ውስተ መካን ቅዱስ ወዘያነብብ ለይለቡ
ይእተ አሚረ እለ ውስተ ይሁዳ ይጕዩ ውስተ አድ
ባር ።

ያገኙ ሁሉ ከትረፋቸው አግብተዋል ፤ እሷ ግን ከድ ፴፬
ኅነቷ ያላትን ሁሉ ንብረቷን ሁሉ አግብታለችና ።
፪ ቆሮ ፰ ፲፪ ።

ምዕራፍ ፲፫ ፤

ክፍል ፷፩ ፤ ስለ ኢየሩሳሌምና

ስለ ቤተ መቅደሱ መፍረስ ።

ከምኵራብ በወጣ ጊዜ ከደቀ መዛሙርቱ አንዱ ፩
መምህር፤ እይ ሕንፃውና ድንጊያው ምን ይመስላል?
አለው ። ሉቃ ፳፩ ፭ ።

ጌታ ኢየሱስም መልሶ ይህን ታላቅ ሕንፃ ታያለህን? ፪
እዚህ የማይፈርስ ሆኖ ድንጊያ በድንጊያ ላይ አይ
ቀርም ።

በደብረ ዘይትም በምኵራብ ፊት ለፊት ተቀምጦ ፫
ሳለ ጴጥሮስና ያዕቆብ ፤ ዮሐንስና እንድርያስ ለብቻ
ቸው ጠየቁት ።

እንዲህም አሉት ንገረን ይህ መቼ ይሆናል? ይህ ፬
ሁሉ በሚደረግበት ጊዜስ ምልክቱ ምንድር ነው?

ጌታ ኢየሱስም መልሶ እንዲህ ይላቸው ጀመረ ፭
ዕወቁ እንዳያስቷችሁ ።

ብዙዎች እኔ ክርስቶስ ነኝ እያሉ በስሜ ይመጣሉና ፮
ብዙዎችንም ያስቷቸዋልና ።

ሰልፉንና የሰልፉን ወሬ በሰማችሁ ጊዜ አትደንግጡ ፯
ይህ ይሆን ዘንድ አለውና ፤ ነገር ግን ወዲያውኑ
የሚፈጸም አይደለም ።

ሕዝብ በሕዝብ ላይ ይነሣል ፤ ነገሥታትም በነገሥ ፰
ታት ላይ ይነሣሉ ፤ በየሀገሩ ድብልቅልቅ ይሆናል ፤
ረኃብም ይመጣል ።

ይህ የመከራው መጀመሪያ ነው ፤ እናንተ ግን ለራሳ ፱
ችሁ ዕወቁ ፤ ወደ አደባባይ ይወስዷችኋል ፤ በየምኵ
ራቡ ይገርፏችኋል ፤ ስለ እኔም ወደ አለቆች ወደ
ነገሥታት ያደርሷችኋል ምስክር ሊሆንባቸው ።
ማቴ ፲ ፲፯ - ፳፪ ።

ለአሕዛብም ሁሉ አስቀድሞ ወንጌልን ሊሰብኩ ይገ ፲
ባል ። ምዕ ፲፮ ፲፭ ።

አሳልፈው በሰጧችሁም ጊዜ አስቀድማችሁ የምት ፲፩
ሉትን የምትናገሩትን አታስቡ ፤ ያናገራችሁንም ያን
ጊዜ ተናገሩ መንፈስ ቅዱስ ነው እንጂ እናንተ
የምትናገሩ አይደላችሁምና ።

ወንድም ወንድሙን ለሞት አሳልፎ ይሰጣል ፤ አባ ፲፪
ትም ልጁን ፤ ልጆችም በወላጆቻቸው ላይ ይነሣሉ
ይገድሏቸዋልም ።

ስለ እኔ ስም በሰው ሁሉ ዘንድ የተጠላችሁ ትሆናላ ፲፫
ችሁ ፤ ትዕግሥትን አዘውትሮ የያዘ ግን እሱ ይድናል ።

በነቢዩ በዳንኤል የተነገረውን መፍረሱ ያመጣውን ፲፬
ጉስቁልና ባያችሁ ጊዜ በቅዱሱ ቦታ ላይ ቆሞ
የሚያነበው ያስተውል ፤ ያን ጊዜም በይሁዳ ያሉ
ወደ ተራሮች ይሽሹ ። ዳን ፱ ፳፯ ። ፲፪ ፱ - ፲ ።

፲፭ ወዘኒ ውስተ ናሕስ ኢይረድ ውስተ ቤት ይባእ ይንሣእ ዘከነ ውስተ ቤት ።

፲፮ ወዘኒ ገዳመ ሀሎ ኢይትመየጥ ድኅሬሁ ይንሣእ ልብሶ ።

፲፯ ወሀለዉ አሌ ሎን ለጽንሳት ወለእለ የሐንፃ ይእተ አሚረ ።

፲፰ ወጸልዩ ከመ ኢይኩን ጕይይክሙ በክረምት ።

፲፱ እስመ ይከውን ይእተ አሚረ ዐቢይ ሕማም ዘእምአመ ክነ ዓለም ኢከነ ከማሁ ፡ ወእምአመ ፈጠረ እግዚአብሔር ዓለመ ኢከነ ወኢይከውንኒ ።

፳ ወሶበ አከ ዘአኅፀርን እግዚአብሔር ለእማንቱ መዋዕል እምኢድኅነ ኵሉ ዘሥጋ ፡ ወባሕቱ በእንተ ኅሩያኒሁ እለ ኀረየ እግዚአብሔር የኃፅሮ እማንቱ መዋዕል ።

፳፩ ወይእተ አሚረ እመቦ ዘይቤለክሙ ነዋ ዝየ ሀሎ ክርስቶስ ፡ ወነዋ ከሐከ ኢትእመኑ ።

፳፪ እስመ ይመጽኡ ሐሳውያነ መሲሕ ፡ ወሐሳውያነ ነቢያት ፡ ወይገብሩ ተአምረ ወመንክረ ከመ ያስሕቱ ፤ ወሶበሰ ይትከሀሎሙ እምአስሐትዎሙ ለኅሩያንሂ ።

፳፫ ወአንትሙሰ ዑቁ ናሁ አቅደምኩ ነጊሮትክሙ ኵሎ ።

ክፍል ፷ወ፪ ፡ በእንተ ምጽአቱ ለወልደ እጓለ እመሕያው ።

፳፬ ወባሕቱ ይእተ አሚረ ምስለ ዝ ኵሉ ሕማም ፀሐይ ይጸልም ፡ ወወርኀኒ ኢይሁብ ብርሃና ።

፳፭ ወከዋክብትኒ ይወድቁ እምሰማይ ወይትሀወክ ኃይለ ሰማያት ።

፳፮ ወእሚሃ ይሬእይዎ ለወልደ እጓለ እመሕያው እንዘ ይመጽእ በደመና ምስለ ኃይል ወብዙኅ ስብሐት ።

፳፯ ወይእተ አሚረ ይፌንዎሙ ለመላእክቲሁ ወያስተጋብእዎሙ ለኅሩያኒሁ እምአርባዕቱ ነፋሳት ወእምአጽናፈ ምድር እስከ አጽናፈ ሰማይ ።

፳፰ ወእምበለስ አእምሩ አምሳሊሁ እምከመ ከነ ዐጽቃ ድኩመ ወሠረፀ ቈጽላ ይትዐወቅ ከመ ልጹቀ ማእረር ።

፳፱ ከማሁኬ አንትሙኒ እምከመ ርኢክሙ ዘንተ ኵሎ ከመ ክነ አእምሩ ከመ ልጽሐ ኀበ ኆኅት ።

፴ አማን እብለክሙ ከመ ኢተኃልፍ ዛቲ ትውልድ ዘእንበለ ይኩን ዝንቱ ኵሉ ።

፴፩ ሰማይ ወምድር የኃልፍ ወቃልየሰ ኢየኃልፍ ።

ክፍል ፷ወ፫ ፡ በእንተ ሰዓት ወዕለት ።

፴፪ ወበእንተሰ ይእቲ ዕለት ወይእቲ ሰዓት አልቦ ዘየአምራ ኢመላእክተ ሰማይ ወኢወልድ ዘእንበለ አብ ባሕቲቱ ።

፴፫ ዑቁ ትጉሁ ወጸልዩ እስመ ኢተአምሩ ማእዜ መዋዕለ ጊዜሁ ።

በሰገነት ላይ ያለም ወደ ምድር ቤት አይውረድ በቤት ውስጥ ያለውንም ይወስድ ዘንድ አይግባ ። ፲፭

በዱር ያለም ልብሱን ይወስድ ዘንድ ወደ ኋላው አይመለስ ። ፲፮

ነገር ግን በዚያ ወራት ለጽንሱና ወልደውም ለሚያሳድጉ ወዮላቸው ። ፲፯

ሽሽታችሁም በክረምት እንዳይሆን ጸልዩ ። ፲፰

ያን ጊዜ ዓለም ከተፈጠረ ጀምሮ እንደሱ ያልሆነ እግዚአብሔርም ከፈጠረ ጀምሮ ያልተደረገ እንግዲህም የማይደረግ ጽኑ መከራ ይሆናልና ። ዳን ፲፪ ፩ ። ፲፱

እግዚአብሔር እነዚያን ቀኖች ባያሳጥራቸው ኖሮ ሥጋ የለበሰ ሁሉ ባልዳነም ነበር ፤ ነገር ግን እግዚአብሔር ስለ መረጣቸው ደጋግ ሰዎች እነዚያ ቀኖች ያጥራሉ ። ፳

ያን ጊዜ ክርስቶስ ከዚህ አለ ወይም ከዚያ አለ የሚሏችሁ ቢኖር አትመኑ ። ፳፩

መሲሕን የሚያስተባብሉ ነቢያትንም የሚያስተባብሉ ይመጣሉና ፤ ለማሳትም ተአምራትና ድንቅ ድንቅ ሥራ ያደርጋሉና ቢቻላቸውስ የተመረጡትንም ባሳቷቸው ነበር ። ፳፪

እናንተ ግን ተጠንቀቁ ፤ እነሆ ሁሉን አስቀድሜ ነግሬአችኋለሁና ። ፳፫

ክፍል ፷፪ ፤ ስለ ሰው ልጅ መምጣት ።

ነገር ግን ያን ጊዜ ከዚህ ሁሉ መከራ ጋር ፀሐይ ይጨልማል ፤ ጨረቃም ብርሃኑን አይሰጥም ። ፳፬

ከዋክብትም ከሰማይ ይወድቃሉ የሰማያትም ኃይል ይናወጣል ። ፳፭

ያን ጊዜም የሰውን ልጅ በኃይልና በብዙ ክብር በደመና ሲመጣ ያዩታል ። ፳፮

ያን ጊዜም መልእክተኞቹን ይልካቸዋል የተመረጡትንም ከዳር እስከ ዳር ከአራቱ መዓዝን ይሰበስቧቸዋል ። ማቴ ፲፫ ፵፩ ። ፳፯

ምሳሌውንም ከበለስ ዕወቁ ጫፏ ያቈጠቈጠ ቅጠሏ ያፈጠፈጠ እንደሆነ መከር እንደ ደረሰ ይታወቃል ። ማቴ ፳፬ ፴፪ ። ፳፰

እንዲሁ እናንተም ይህ ሁሉ እንደሆነ ባያችሁ ጊዜ ከደጃፍ እንደ ደረሰ ዕወቁ ። ፳፱

ይህ ሁሉ ሳይደረግ ይህች ትውልድ እንደማታልፍ እውነት እላችኋለሁ ። ፴

ሰማይና ምድር ያልፋል ፤ ቃሌ ግን አያልፍም ። ፴፩

ክፍል ፷፫ ፤ ስለ ሰዓትና ስለ ዕለት ።

ያቺን ዕለት ያቺን ሰዓት ግን የሚያውቃት የለም መላእክትም ቢሆኑ ልጅም ያለ አባት ብቻውን ። ፴፪

እወቁ ትጉ ጸልዩ ጊዜው ዘመኑ መቼ እንደሆነ አታውቁምና ። ፴፫

፴፬ እስመ ከመ ብእሲ ዘይነግድ ወየኃድግ ቤቶ ወይሁቦሙ ግብሮሙ ለአግብርቲሁ ለለአሐዱ እምኔሆሙ ወይኤዝዞ ለዐፃዊኒ ከመ ይትጋህ ።

፴፭ ትግሁ እንከ እስመ ኢተአምሩ ማእዜ ይመጽእ በዓለ ቤት፤ እመኒ ሠርከ፤ ወእመኒ መንፈቀ ሌሊት፤ ወእመኒ ጊዜ ይነቁ ዶርሆ፤ ወእመኒ ጸቢሐ ።

፴፮ ኢይምጻእክሙ ግብተ ወኢይርከብክሙ እንዘ ትነውሙ ።

፴፯ ወናሁ እብለክሙ ለኵልክሙ ትግሁ ።

ምዕራፍ ፲ወ፬፤

ክፍል ፷ወ፩፤ በእንተ ዘከመ መከሩ ሊቃነ ካህናት ይቅትልዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ።

፩ ወእስከ ሰኑይ መዋዕል ፋሲካ በዓለ መጸለት ወኃሠሡ ሊቃነ ካህናት ወጸሐፍት ይትመየንዎ ወየአኅዝዎ ወይቅትልዎ ።

፪ ወይቤሉ አኮ በበዓል ከመ ኢይትሀወክ ሕዝብ ።

ክፍል ፷ወ፪፤ በእንተ እንተ ቀብአቶ ለእግዚእን ዕፍረት ።

፫ ወእንዘ ሀሎ ቢታንያ በቤተ ስምዖን ዘለምጽ እንዘ ይረፍቅ፤ መጽአት ብእሲት ወእምጽአት ዕፍረተ ዘአልባስጥሮስ ዘናርዱ ቅድው ዘዕፁብ ሤጡ ወአክሰቶ ወሰጠት ዲበ ርእሱ ።

፬ ወቦ እለ ተምዑ ወይቤሉ፤ ለምንት ዘመጠነዝ ሐጕል ዘዝ ዕፍረት ።

፭ እምኢትከሀሎኑ ይሠየጥ ዝንቱ ዕፍረት ፈድፋደ እምሠለስቱ ምእት ዲናር ወይትወሀብ ለነዳያን፤ ወገሠፅዋ ።

፮ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ኅድግዋ ለብእሲት ወኢታሥርኅዋ ሠናየ ግብረ ገብረት ላዕሌየ ።

፯ ወለነዳያንሰ ዘልፈ ትረክብዎሙ ወጊዜ ፈቀድክሙ ታሤንዩ ሎሙ፤ ወኪያየሰ አኮ ዘልፈ ዘትረክቡኒ ።

፰ ወዘቦቱ ዘበቲ ገብረት ወአቅደመት ወቀብዐተኒ ሥጋየ ለቀበርየ ።

፱ አማን እብለክሙ ኀበ ሰበክዋ ለዛቲ ወንጌል ውስተ ኵሉ ዓለም ይነግሩ ዘገብረት ዛቲ ብእሲት ወይዜከርዋ ።

ክፍል ፷ወ፫፤ በእንተ ዘከመ ሤጠ ለእግዚእ ።

፲ ወይሁዳ አስቆሮታዊ አሐዱ እምዐሠርቱ ወክልኤቱ ሖረ ኀበ ሊቃነ ካህናት ከመ ያግብኦ ሎሙ ።

ቤቱን ትቶ ለአገልጋዮቹም ከነሱ ለያንዳንዱ ሥራቸውን ሰጥቶ በረኛውንም እንዲተጋ አዝዞ ወደ ሩቅ አገር እንደሚሄድ ሰው ነውና ። ማቴ ፳፭ ፲፬ ። ሉቃ ፲፱ ፲፪ ። ፴፬

እንግዲህ ትጉ ባለቤት መቼ እንደሚመጣ አታውቁምና ማታም እንደሆነ፤ በመንፈቀ ሌሊትም እንደ ሆነ፤ ዶሮ ሲጮኽም እንደሆነ፤ ጧትም እንደሆነ ። ሉቃ ፲፪ ፴፰ ። ፴፭

ድንገት እንዳይመጣባችሁ ተኝታችሁም እንዳያገኛችሁ ። ፴፮

እነሆ ሁላችሁንም ትጉ እላችኋለሁ ። ፴፯

ምዕራፍ ፲፬ ።

ክፍል ፷፩፤ ጌታ ኢየሱስን ይገድሉት ዘንድ የካህናት አለቆች እንደ መከሩ ።

ከሁለት ቀንም በኋላ በዓለ ፋሲካ ነበረ፤ የካህናት አለቆችና ጸሐፎችም ሊተናኰሉት ሊይዙትና ሊገድሉት ይሹ ነበር ። ማቴ ፳፮ ፩-፭ ። ዮሐ ፲፫ ፩-፳ ። ሉቃ ፳፪ ፩ ። ፩

ነገር ግን ሕዝቡ እንዳይታወኩ በበዓል አይሆንም አሉ ። ማቴ ፳፮ ፭ ። ፪

ክፍል ፷፪፤ ጌታችንን ሽቱ ስለ ቀባቸው ሴት ።

በቢታንያም በለምጻሙ በስምዖን ቤት ለምሳ ተቀምጦ ሳለ አንዲት ሴት መጥታ እጅግ ያማረ ዋጋው የከበረ ናርዶስ የሚባል አንድ ብልቃጥ ሽቱ አመጣችና አዋሕዳ በራሱ ላይ አፈሰሰችው ። ማቴ ፳፮ ፮ ፲፫ ። ዮሐ ፲፪ ፩-፰ ። ፫

እንዲህ ብለው የተቈጡም አሉ የዚህ ሽቱ ጥፋት ይህን ያህል ለምንድነው? ፬

ይህ ሽቱ ከሦስት መቶ ወቄት በላይ ተሽጦ ለነዳያን ሊሰጥ ባልተቻለም ነበርን! እሷንም ገሠጿዋት ። ፭

ጌታ ኢየሱስም እንዲህ አላቸው ሴቲቱን ተዉዋት አታዳክሙዋት ለእኔ መልካም ሥራ ሠርታለች ። ፮

ነዳያንንስ ዘወትር ታገኙዋቸዋላችሁ በወደዳችሁም ጊዜ ትቸሩላቸዋላችሁ እኔን ግን ዘወትር የምታገኙኝ አይደለም ። ዘዳግ ፲፭ ፲፩ ። ፯

ይህችም ያላትን አደረገች አስቀድማም ለመቃብሬ ሥጋዬን ቀባች ። ፰

እውነት እላችኋለሁ ወንጌልን በሚሰብኩበት በታ ሁሉ ይህች ሴት ያደረገችውን ይናገሩላታል ያስቧታል ። ፱

ክፍል ፷፫፤ ጌታውን ስለ ሸጠ ሰው ።

ከዐሥራ ሁለቱ አንዱ ያስቆሮቱ ሰው ይሁዳም ለነሱ አሳልፎ ይሰጣቸው ዘንድ ወደ ካህናት አለቆች ሄደ ማቴ ፳፮ ፲፬-፲፮ ። ሉቃ ፳፪ ፫-፯ ። ፲

፲፩ ወሰሚዖሙ ተፈሥሑ ወተናገርዎ የሀብዎ ሠሉሳ ብሩረ ፤ ወፈቀደ በጽሚት ያግብኦ ሎሙ ።

## ክፍል ፳ወ፯፤ በእንተ ፋሲካ ።

፲፪ ወአመ ቀዳሚት ዕለት በዓለ መጸለት ፋሲካ አመ ይጠብሑ ፋሲሐ ይቤልዎ አርዳኢሁ በአይቴ ትፈቅድ ናስተዳሉ ለከ ትብላዕ ፋሲሐ ።

፲፫ ወፈነወ ክልኤተ እምአርዳኢሁ ወይቤሎሙ ሑሩ ሀገረ ዘቅድሜክሙ ወትረክቡ ብእሴ ዘይጸውር ጻሕበ ማይ ወትልውዎ ኀበ ቦአ ቤተ ።

፲፬ ወበልዎ ለበዐለ ቤት ይቤለከ ሊቅ አይቴ ጽርሕ ኀበ እበልዕ ፋሲሐ ምስለ አርዳእየ ።

፲፭ ወውእቱ ያርእየክሙ ጽርሐ ዐቢየ ወንጡፈ ወር ሡየ ፤ ወበህየ አስተዳልዉ ለነ ።

፲፮ ወሖሩ አርዳኢሁ ሀገረ ወረከቡ በከመ ይቤሎሙ ወአስተዳለዉ በህየ ፋሲሐ ።

፲፯ ወመስዮ ሖረ ምስለ ዐሠርቱ ወክልኤቱ አርዳኢሁ ።

## ክፍል ፳ወ፰፤ በእንተ ከሢቶቱ ለሐዋርያት ዘያገብኦ ።

፲፰ ወእንዘ ይረፍቁ ወይበልዑ ይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አማን እብለክሙ አሐዱ እምኔክሙ ዘይበልዕ ምስሌየ ያገብአኒ ።

፲፱ ወአኀዙ ይተክዙ ወይበሉ በበአሐዱ አነኑ እንጋ ውእቱ ።

፳ ወአውሥአ ወይቤሎሙ አሐዱ እምዐሠርቱ ወክል ኤቱ ዘይጸብሕ ምስሌየ ውስተ መጽብሕየ ።

፳፩ ወወልደ እጓለ እመሕያውሰ የሐውር በከመ ጽሑፍ በእንቲአሁ ፤ ወባሕቱ አሌ ሎቱ ለውእቱ ብእሲ ዘእ ምኔሁ ይትሜጠውዎ ለወልደ እጓለ እመሕያው እም ኀየሰ ሶበ ኢተወልደ ለውእቱ ብእሲ ።

## ክፍል ፳ወ፱፤ በእንተ ሥርዓተ ምሥጢር ።

፳፪ ወእንዘ ይበልዑ ነሥአ እግዚእ ኢየሱስ ኅብስተ ወባረከ ወፈተተ ወወሀበሙ ወይቤሎሙ ንሥኡ ብልዑ ዝ ውእቱ ሥጋየ ።

፳፫ ወነሥአ ጽዋዐኒ ወአእኰተ ወወሀበሙ ወይቤሎሙ ንሥኡ ወሰትዩ እምኔሁ ኵልክሙ ።

፳፬ ወይቤሎሙ ዝ ውእቱ ደምየ ዘሐዲስ ሥርዓት ዘይ ትከዐው በእንተ ብዙኃን ።

፳፭ አማን እብለክሙ ኢይሰቲ እንከ እምዝንቱ ፍሬ ወይን እስከ እንታክቲ ዕለት አመ እሰትዮ ሐዲሰ በመንግሥተ እግዚአብሔር ።



ሰምተውም ደስ አላቸውና ሠላሳ ብር ሊሰጡት ተዋ ፲፩
ዋሉት፤ በምሥጢርም አሳልፎ እንዲሰጣቸው ምቹ ጊዜ ይሻ ነበረ ።

## ክፍል ፳፯ ፤ ስለ ፋሲካ ።

በጉን በሚያርዱበት ፋሲካ በምትባለው በቂጣ በዓል ፲፪
በመጀመሪያይቱ ቀን ደቀ መዛሙርቱ ፋሲካን ትበላ ዘንድ በየት ልናዘጋጅልህ ትወዳለህ? አሉት ። ማቴ ፳፮ ፤ ፲፯ - ፳፱ ፡ ሉቃ ፳፪ ፤ ፯ - ፲፫ ።

ከደቀ መዛሙርቱም ሁለቱን ላካቸው እንዲህም አላ ፲፫
ቸው በፊታችሁ ወደ አለችው ሀገር ሂዱና የውኃ ማድጋ የተሸከመ ሰው ታገኛላችሁ ተከተሉት ።

ወደ ገባበት ቤትም ገብታችሁ ባለቤቱን መምህር ፲፬
ከደቀ መዛሙርቴ ጋር ፋሲካን የምበላበት ወደት ነው ብሎሃል? በሉት ። ምሳ ፲፩ ፤ ፫ ።

እርሱ የተነጠፈ ፣ የተጋረደ ፣ ታላቅ አዳራሽ ያሳያች ፲፭
ኋል ፤ በዚያ አዘጋጁልን ።

ደቀ መዛሙርቱም ወደ ከተማ ሄዱ ፤ እንዳላቸውም ፲፮
አገኙና በዚያም ፋሲካን አዘጋጁ ።

በመሸም ጊዜ ከዐሥራ ሁለቱ ደቀ መዛሙርቱ ፲፯
ጋር ሄደ ።

## ክፍል ፳፰ ፤ የሚያስይዘውም ለሐዋርያት ስለ መግለጡ ።

በማእድም ላይ ተቀምጠው ሲበሉ ጌታ ኢየሱስ በእ ፲፰
ውነት እላችኋለሁ ከእናንተ አንዱ ከእኔ ጋር የሚበላው ያስይዘኛል አላቸው ።

እያንዳንዱ ያዝኑ ይተክዙ እኔ እሆን እኔ እሆን? ፲፱
ይሉ ጀመር ። ዮሐ ፲፫ ፤ ፳፩ - ፳፯ ።

እርሱም መልሶ እንዲህ አላቸው ፤ ከዐሥራ ሁለታ ፳
ችሁ አንዱ ከኔ ጋር ከወጭቱ የሚጠልቀው ነው ።

የሰው ልጅስ ስለርሱ እንደ ተጻፈ ይሄዳል ፤ ነገር ፳፩
ግን የሰውን ልጅ ከእጁ ለሚቀበሉት ለዚያ ሰው ወዮለት ፤ ለዚያ ሰው ባልተወለደ ይሻለው ነበር ።

## ክፍል ፳፱ ፤ ስለ ሥጋውና ደሙ ሥርዓት ።

ሲበሉም ጌታ ኢየሱስ ኅብስቱን አንሥቶ ባርኮ ፳፪
ፈትቶ እንኩ ብሉ ይህ ሥጋዬ ነው ብሎ ሰጣቸው ። ሉቃ ፳፪ ፤ ፳፩ - ፳፫ ። ዮሐ ፲፫ ፤ ፲፰ - ፴፪ ።

ጽዋዉንም አንሥቶ ባርኮ ሁላችሁም እንኩ ከእሱ ፳፫
ጠጡ ብሎ ሰጣቸው ። ፩ ቆሮ ፲፩ ፤ ፳፫ - ፴ ።

እንዲህም አላቸው ስለ ብዙዎች የሚፈሰው አዲስ ፳፬
ሥርዓት የሚጸናበት ደሜ ይህ ነው ። ፩ ቆሮ ፲፩ ።

እውነት እላችኋለሁ በእግዚአብሔር መንግሥት ፳፭
አዲስ አድርጌ እስክጠጣበት እስከዚያች ቀን ድረስ እንግዲህ ከዚህ የወይን ጭማቂ አልጠጣም ። ማቴ ፳፮ ፤ ፳፮ - ፴ ። ሉቃ ፳፪ ፤ ፲፬ - ፳ ።

## ክፍል ፸ ፡ በእንተ ዝርወተ ሐዋርያት ።

፳፮ ወሰቢሖሙ ወእንቢቦሙ ወፅኡ ውስተ ደብረ ዘይት ።
፳፯ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ኵልክሙ ትክሕዱኒ
በዛቲ ሌሊት እስመ ጽሑፍ ዘይብል እቀትሎ ለኖ
ላዊ ወይዘረዉ አባግዒሁ ።

፳፰ ወእምድኅረ ተንሣእኩ እቀድመክሙ ገሊላ ።

፳፱ ወይቤሎ ጴጥሮስ ለእመኒ ኵሎሙ ክሕዱከ አንሰ
ኢይክሕደከ ።
፴ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ አማን እብለከ አንተ ትክ
ሕደኒ ዮም ሥልሰ በዛቲ ሌሊት ዘእንበለ ይንቁ
ዶርሆ ክልኤ ጊዜ ።
፴፩ ወአፈድፈደ ጴጥሮስ ትምክሕተ ወተኃበርተ እንዘ
ይብል እመውትኒ ምስሌከ ወኢይክሕደከ፡ ወከማሁ
ይቤሉ ኵሎሙ ።

## ክፍል ፸ወ፩ ፡ በእንተ ጸሎቱ በጌቴሴማን ።

፴፪ ወሖሩ ዓፀደ ወይን እንተ ስማ ጌቴሴማኒ ወይቤ
ሎሙ ለአርዳኢሁ ንበሩ ዝየ እስከ አሐውር ከሐ
ወእጼሊ ።
፴፫ ወነሥኦሙ ለጴጥሮስ ወለያዕቆብ ወለዮሐንስ ወአ
ኀዘ ይተክዝ ወይኄዝን ።
፴፬ ወይቤሎሙ ተከዘት ነፍስየ እስከ ለሞት ንበሩ ዝየ
ወትግሁ አንከ ።
፴፭ ወእምዝ ተአተተ ሕቀ ወሰገደ ውስተ ምድር ወጸ
ለየ ከመ ትኅልፍ እምኔሁ ይእቲ ሰዓት ለእመ ይት
ከሀል ።
፴፮ ወይቤ አባ ወአቡየ ኵሉ ይትከሀለከ አኅልፋ እም
ኔየ ለዛቲ ጽዋዕ ወባሕቱ ፈቃደ ዚአከ ለይኩን
ወአኮ ፈቃደ ዚአየ ።
፴፯ ወገቢኦ ረከቦሙ እንዘ ይነውሙ ወይቤሎ ለጴጥሮስ
ስምዖን ትነውምኑ ወኢትክል ተዐቅሦ አሐተ ሰዓተ ።

፴፰ ትግሁ ወጸልዩ ከመ ኢትባኡ ውስተ መንሱት፡
እስመ መንፈስ ይፈቅድ ወሥጋ ይደክም ።
፴፱ ወሖረ ካዕበ ወጸለየ ወኪያሁ ከመ ይቤ ።
፵ ወገቢኦ ካዕበ ረከቦሙ እንዘ ይነውሙ እስመ ከብዳ
አዕይንቲሆሙ ወኢየአምሩ ዘይነብቡ ።
፵፩ ወመጽአ በሣልስ ወይቤሎሙ ኑሙ እንከሰ ወአዕ
ርፉ ምዕረ፡ እስመ፡ናሁ በጽሐ ጊዜሁ ወናሁ ያገብእዎ
ለወልደ እጓለ እመሕያው ውስተ እደ ኃጥኣን ።

፵፪ ተንሥኡ ንሑር ናሁ በጽሐ ዘያገብአኒ ።



## ክፍል ፸፤ ስለ ሐዋርያት መበተን ።

አመስግነው ዘምረው ወደ ደብረ ዘይት ወጡ ። ፳፮
ጌታ ኢየሱስም ደቀ መዛሙርቱን እንዲህ አላቸው ፳፯
በዚች ሌሊት ሁላችሁ ትክዱኛላችሁ "ጠባቂውን
እገድለዋለሁ በጎቹም ይበተናሉ የሚል ጽሑፍ
አለና „ ዘካ ፲፫ ፯ ። ማቴ ፳፮ ፴-፴፭ ። ዮሐ ፲፮ ፴፪ ።
ከተነሣሁም በኋላ ወደ ገሊላ እቀድማችኋለሁ ። ፳፰
ምዕ ፲፮ ፯ ።
ጴጥሮስም ሁሉም ቢክዱህ እንኳን እኔ አልክድህም ፳፱
አለው ።
ጌታ ኢየሱስም እውነት እልሃለሁ ዶሮ ሁለት ጊዜ ፴
ሳይጮኽ አንተ ሦስት ጊዜ ትክደኛለህ አለው ።
ዮሐ ፲፫ ፴፰ ።
ጴጥሮስም ካንተ ጋር እሞታለሁ እንጂ አልክድህም ፴፩
እያለ ትምክሕትንና ድፍረትን አበዛ ሁሉም እንደሱ
አሉ ።

## ክፍል ፸፩፤ በጌቴሴማን ስለ መጸለዩ ።

ጌቴሴማኒ ወደምትባለው የወይን ቦታም ሄዱ ደቀ ፴፪
መዛሙርቱንም ወደዚያ ሂጄ እስክጸልይ ድረስ ከዚህ
ቆዩ አላቸው ፡ ማቴ ፳፮ ፴፮ ፵፮ ። ሉቃ ፳፪ ፵፩ ፵፮
ጴጥሮስን ያዕቆብንና ዮሐንስን ከእሱ ጋር ወሰዳቸው ፴፫
ያዝንና ይተክዝም ጀመር ።
ነፍሴ እስከ ሞት ድረስ አዘነች ከዚህ ሁኑና እንግ ፴፬
ዲህ ትጉ አላቸው ፡ ዮሐ ፲፪ ፳፯ ።
ከዚህም በኋላ ጥቂት እልፍ ብሎ ከምድር ላይ ሰግዶ ፴፭
ይቻል እንደሆነ ያቺ ሰዓት ከእሱ ታልፍ ዘንድ ጸለየ።

አባ አባቴ ሆይ ! ሁሉ ይቻልሃል ይህቺን ጽዋ ከእኔ ፴፮
አሳልፋት ግን የኔ ፈቃድ ያይደለ ያንተ ፈቃድ
ይሁን አለ ።
በተመለሰም ጊዜ ተኝተው አገኛቸውና ጴጥሮስን ፴፯
እንዲህ አለው ፤ ስምዖን ታንቀላፋለህን አንዲት ሰዓ
ት ስንኳ መታገሥ አትችልምን ?
ወደ ፈተና እንዳትገቡ ተግታችሁ ጸልዩ መንፈስ ፴፰
ሲሻ ሥጋ ይደክማልና ።
ዳግመኛም ሄዶ ያንኑ ቃል ብቻ ጸለየ ። ፴፱
ዳግመኛም ተመልሶ ተኝተው አገኛቸው ዓይናቸው ፵
ፈዝው ነበርና የሚናገሩትንም አያውቁም ነበርና ።
በሦስተኛውም መጥቶ እንዲህ አላቸው እንግዲህስ ፵፩
ተኙ እንደኛችሁን ዕረፉ አሁን ጊዜው ደርሶአልና
እነሆ የሰውን ልጅ በኃጥአን እጅ አሳልፈው ይሰ
ጡታል ።
ተነሡ እንሂድ እነሆ የሚያስይዘኝ መጥቷል ። ፵፪

## ክፍል ፸ወ፪ ፡ በእንተ ዘከመ አግብአ ይሁዳ ለእግዚእነ ።

፵፫ ወእንዘ ይትናገሮሙ በጽሐ ሶቤሃ ይሁዳ አስቆሮታዊ አሐዱ እምዐሠርቱ ወክልኤቱ ወምስሌሁ ብዙኃን ሰብእ ምስለ መጣብሕ ወዕፀው እምኀበ ሊቃነ ካህናት ወጸሐፍት ወረበናት ።

፵፬ ወወሀቦሙ ትእምርተ ዘያገብአ ወይቤሎሙ ዘሰዐምክዎ ውእቱ አኀዝዎ ወአጽንዕዎ ወሰድዎ ።

፵፭ ወሶቤሃ መጽአ ኀቤሁ ወይቤሎ ረቢ ወሰዐሞ ።
፵፮ ወሰፍሑ እደዊሆሙ ላዕሌሁ ወአኀዝዎ ።
፵፯ ወመልሐ መጥባሕቶ አሐዱ እምእለ ምስሌሁ ይቀውሙ ወዘበጦ ለገብረ ሊቀ ካህናት ወመተረ ዕዝኖ ።

፵፰ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ ከመ ሰራቂኑ ትዴግኑኒ መጻእክሙ ምስለ መጣብሕ ወአብትር ተአኀዙኒ ።
፵፱ ወኵሎ አሚረ ሀሎኩ ምስሌክሙ እሜህር በምኵራብ ወኢአኀዝክሙኒ ፡ ወባሕቱ ከመ ይብጻሕ ዘውስተ መጻሕፍት ።
፶ ወኃደግዎ ኵሎሙ አርዳኢሁ ወጐዩ ።
፶፩ ወተለዎ አሐዱ ወሬዛ ዘይትዓጸፍ ሰንዱነ ወአኀዝዎ ወራዙት ።
፶፪ ወኀደገ ሰንዱኖ ወጐየ ዕራቆ ።

## ክፍል ፸ወ፫ ፡ በእንተ ቀዊሞቱ ውስተ ዓውድ ።

፶፫ ወወሰድዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ኀበ ሊቀ ካህናት ወተጋብኡ ኀቤሁ ኵሎሙ ሊቃነ ካህናት ወጸሐፍት ወረበናት ።

፶፬ ወተለዎ ጴጥሮስ እምርኁቅ ውስተ ውሣጤ ዓፀደ ሊቀ ካህናት ወነበረ ምስለ ወዐልያኒሆሙ ይስሕን መንገለ በርህ ።
፶፭ ወኃሠሡ ሊቃነ ካህናት ወኵሉ ዐውድ ሰማዕተ ሐሰት በዘያስተዋድይዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ከመ ይቅትልዎ ወኃጥኡ ።
፶፮ ወብዙኃን እለ አስተዋደይዎ ወኢኀብረ ቃሎሙ ።

፶፯ ወቦ ሰማዕተ ሐሰት እለ ተንሥኡ ወነበቡ ሐሰተ ።

፶፰ ወይቤሉ ንሕነ ሰማዕናሁ እንዘ ይብል አነ እነሥቶ ለዝንቱ ቤተ መቅደስ ዘእድ ገብሮ ወበሠሉስ ዕለት አሐንጽ ካልአ ዘእድ ኢገብሮ ።

፶፱ ወምስለ ዝኒ ኢኀብረ ስምዖሙ ።
፷ ወተንሥአ ሊቀ ካህናት ወሐተቶ ለእግዚእ ኢየሱስ



## ክፍል ፸፪ ፡ ይሁዳ ጌታችንን እንዳስያዘው ።

ሲነጋገራቸውም ወዲያውኑ ከዐሥራ ሁለቱ አንዱ ፵፫
አስቆሮታዊው ይሁዳ ደረሰ ከእሱም ጋር ከካህናት አለቆች ከጻፎችና ከሽማግሎች የተላኩ ሾተል ጎመድ የያዙ ብዙ ሰዎች ነበሩ ። ዮሐ ፲፰ ፡ ፪ - ፲፩ ። ማቴ ፳፮ ፡ ፵፯ - ፶ ።
የሚያስይዘውንም ምልክት ሰጥቷቸው ነበር ፡ የሳምኩት እርሱ ነው ፤ አጥብቃችሁ ያዙና ውሰዱት አላቸው ። ፵፬
ያን ጊዜም ወደሱ መጣና መምህር ! ብሎ ሳመው ። ፵፭
በእርሱም ላይ እጃቸውን ዘርግተው ያዙት ። ፵፮
ከጌታ ጋር ቆመው ከነበሩትም አንዱ ሰይፉን መዝዞ የሊቀ ካህናቱን ባርያ መታው ጆሮውንም ቈረጠው ። ማቴ ፳፮ ፡ ፵፯ - ፶ ። ፵፯
ጌታ ኢየሱስም መልሶ እንዲህ አላቸው እንደ ሌባ ተከታትላችሁ በሾተል በጐመድ ልትይዙኝ መጣችሁን ! ፵፰
በምኵራብ ሳስተምር ከእናንተ ጋር ነበርኩ አልያዛችሁኝም ፡ ግን በመጽሐፍ ያለው ይፈጸም ዘንድ ነው ። ማቴ ፳፮ ፡ ፶፬ - ፶፮ ። ፵፱
ደቀ መዛሙርቱም ሁሉ ጥለዉት ሸሹ ። ማቴ ፳፮ ፡ ፶፮ ። ፶
ነጠላ የለበሰ አንድ ጐልማሳ ይከተለው ነበር ፤ ጐበዛዝትም ያዙት ። ፶፩
ነጠላውን ትቶ ዕራቆቱን ሸሸ ። ፶፪

## ክፍል ፸፫ ፡ በአደባባይ ስለ መቆሙ ።

ጌታ ኢየሱስንም ወደ ሊቀ ካህናቱ ወሰዱት ፤ የካህናት አለቆች ጻፎችና ሽማግሎችም ከእሱ ዘንድ ተሰበሰቡ ። ማቴ ፳፮ ፡ ፶፯ ። ሉቃ ፳፪ ፡ ፶፬ ። ዮሐ ፲፰ ፡ ፲፫ ። ፶፫
ጴጥሮስም እስከ ካህናቱ አለቃ ግቢ ውስጥ ድረስ ከሩቅ ተከተለው በእሳቱ ፊት ለፊትም ከሎሌዎቹ ጋር ሊሞቅ ተቀመጠ ። ፶፬
የካህናት አለቆችና ሸንጎች ሁሉ ይገድሉት ዘንድ ጌታ ኢየሱስን እንዲከሱት የሐሰት ምስክሮችን ፈለጉ ፡ ግን አጡ ። ዮሐ ፲፰ ፡ ፲፱ - ፳፬ ። ማቴ ፳፮ ፡ ፶፱ ። ፶፭
የከሰሱት ብዙዎች ናቸው ፡ ግን ቃላቸው አንድ አልሆነም ። ፶፮
ተነሥተው በሐሰት የመሰከሩ የሐሰት ምስክሮች ነበሩ ። ፶፯
እኔ ይህን የሰው እጅ የሠራውን ቤተ መቅደስ አፍርሼ በሦስተኛው ቀን እጅ ያልሠራውን ሌላ ቤተ መቅደስ እሠራለሁ ሲል እኛ ሰምተነዋል አሉ ። ዮሐ ፪ ፡ ፲፱ - ፳፩ ። ፶፰
ይህም ቢሆን ምስክርነታቸው አልተባበረም ። ፶፱
ሊቀ ካህናቱም ተነሥቶ ይህን ያህል ሲያሳጡህ የም ፷

ወይቤሎ አልቦኑ ዘትሰጠው እንዘ መጠነዝ ያስተዋ
ድዩከ ።
፷፩ ወአርመመ ወኢተሰጥዎ ወኢምንትኒ፡ ወካዕበ ሐተቶ
ሊቀ ካህናት ወይቤሎ አንተኑ ውእቱ ክርስቶስ
ወልዱ ለቡሩክ ።
፷፪ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ እወ አነ ውእቱ፡ ወትሬ
እይዎ ለወልደ እጓለ እመሕያው እንዘ ይነብር በየ
ማነ ኃይል ወይመጽእ በደመና ሰማይ ።
፷፫ ወሰጠጠ አልባሲሁ ሊቀ ካህናት ወይቤ ምንተ
እንከ ትፈቅዱ ሎቱ ሰማዕተ ።
፷፬ ናሁ ለሊክሙ ሰማዕክሙ ጽርፈቶ ምንተ እንከ
ትብሉ፡ ወአግብኡ ፍትሐ ኵሎሙ ወይቤሉ ይቅ
ትልዎ ።
፷፭ ወአኀዙ እምውስቴቶሙ ይውርቅዎ ወይጽፍዕዎ ገጾ
ወይኰርዕዎ ርእሰ፡ ወይቤልዎ ተነበይ ለነ ክርስቶስ
መኑ ጸፍዐከ፡ ወኮኑ ወዓልት ይጸፍዕዎ በሕቁ ።

ክፍል ፸ወ፬፡ በእንተ ክሕደተ ጴጥሮስ ።

፷፮ ወእንዘ ሀሎ ጴጥሮስ ታሕተ ውስተ ዓፀድ መጽአት
አሐቲ ወለት እምእእማተ ሊቀ ካህናት ።

፷፯ ወርእየቶ ለጴጥሮስ ይስሕን ወነጸረቶ ወትቤሎ፡
አንተሂ ምስለ ኢየሱስ ገሊላዊ ሀለውከ ።

፷፰ ወክሕደ ወይቤላ ኢየአምር ወኢይጤይቅ ዘትብሊ፡
ወወፅአ አፍአ ኀበ ጸናፌ ዓፀድ ወነቀወ ዶርሆ ።

፷፱ ወርእየቶ ካዕበ ካልእት ወትቤሎሙ ለእለ ይቀውሙ
ህየ ዝንቱኒ እምኔሆሙ ውእቱ፡ ወክሕደ ካዕበ ።

፸ ወእምድኅረ ሕቀ ካዕበ ይቤልዎ ለጴጥሮስ እለ ይቀ
ውሙ፡ አማን እምኔሆሙ አንተ ወገሊላዊ አንተ
ወቃልከ ያዔውቀከ፡ ወአኀዘ ይትረገም ወይምሐል
እንዘ ይብል ኢየአምሮ ለውእቱ ብእሲ ዘትብሉ፡
ወሶቤሃ ነቀወ ካዕበ ዶርሆ ።
፸፩ ወተዘከረ ጴጥሮስ ቃሎ ለእግዚእ ኢየሱስ ዘይቤሎ ።

፸፪ ሥልሰ ትክሕደኒ ዘእንበለ ይንቁ ዶርሆ ክልኤ ጊዜ፡
ወበከየ ።

ምዕራፍ ፲ወ፭፡

ክፍል ፸ወ፭፡ በእንተ ቀዊሞቱ ቅድመ ጲላጦስ ።

፩ ወጸቢሖ ተማከሩ ሊቃነ ካህናት ወረበናት ወጸሐ
ፍት ሕዝብ ወኵሉ ዐውድ ወሐመይዎ ለእግዚእ
ኢየሱስ ወወሰድዎ ወመጠውዎ ለጲላጦስ ።

ትመልሰው የለህምን ብሎ ጌታ ኢየሱስን ጠየቀው ።

ዝም አለ ምንም አልመለሰለትም፡ ዳግመኛ ሊቀ ካህ ፷፩
ናቱ የቡሩኩ ልጅ ክርስቶስ አንተ ነህን? አለው ።
ምዕ ፲፫ ፡ ፪ ።
ጌታ ኢየሱስም አዎን እኔ ነኝ፡ የሰው ልጅ በኃይል ፷፪
ቀኝ ሲቀመጥ በሰማይ ደመና ሲመጣ ታዩታላችሁ
አለው ።
የካህናት አለቃም ልብሱን ቀደደ እንዲህም አለ፤ ፷፫
እንግዲህ ምን ምስክር ተፈለጋላችሁ?
እነሆ እናንተ ራሳችሁ ስድቡን ሰማችሁ፡ እንግዲህ ፷፬
ምን ትላላችሁ? ሁሉም ይሙት በቃ ብለው ፈረዱ ።
ዮሐ ፲፱ ፡ ፯ ።
ከመካከላቸውም ይተፉበት፡ በጥፊ ይመቱት፡ ራሱን ፷፭
ይመቱት፡ ክርስቶስ ማን መታህ ንገረን? ይሉት ጀመር
ሎሌዎችም መላልሰው በጥፊ ይመቱት ጀመር ።

ክፍል ፸፬፡ ስለ ጴጥሮስ ክሕደት ።

ጴጥሮስም በግቢው ውስጥ በታች ቤት ሳለ፡ ከሊቀ ፷፮
ካህናቱ ገረዶች አንዲት ብላቴና መጣች ። ማቴ ፳፮፡
፷፱ ። ሉቃ ፳፪ ፡ ፶፮-፷፪ ። ዮሐ ፲፰ ፡ ፲፭-፳፯ ።
ጴጥሮስን እሳት ሲሞቅ አየችው ተመልክታውም፡ ፷፯
አንተም ከገሊላዊው ከኢየሱስ ጋር ነበርክ?
አለችው ።
የምትዪውን አላውቅም፡ ልብ አላደርገውም ብሎ ፷፰
ካደ፡ ከቅፅሩም ወደ ውጭም ወደ መጀመርያ አጥር
ወጣ፡ ዶሮም ጮኸ ።
ዳግመኛም ሴላዪቱ ብላቴና አየችውና ከዚያ ቆመው ፷፱
ለነበሩት ይህም ከእነሱ ወገን ነው አለቻቸውና፡
ሁለተኛ ካደ ።
ከጥቂት ጊዜም በኋላ ከዚያ ቆመው የነበሩት ዳግ ፸
መኛ በእውነት አንተ ከነርሱ ወገን ነህ? አንተ ገሊ
ላዊ ነህ? አነጋገርህም ያስታውቅሃል ።

ያንን የምትሉትን ሰው አላውቀውም እያለ ይምል ፸፩
ይገዝት ጀመር፡ ያን ጊዜም ዶሮ ሁለተኛ ጮኸ ።
ጴጥሮስም ዶሮ ሁለት ጊዜ ሳይጮኽ ሦስት ጊዜ ትክ ፸፪
ደኛለህ ያለውን የጌታ የኢየሱስን ቃል አሰበ፡ አለ
ቀሰም ። ቍ ፡ ፴ ።

ምዕራፍ ፲፭፡

ክፍል ፸፭፡ በጲላጦስ ፊት ስለ መቆሙ ።

በነጋ ጊዜም የካህናት አለቆች ሽማግሎችና የሕ ፩
ዝብ ጻፎች ሸንጎውም ሁሉ ተማከሩና ጌታ ኢየሱ
ስን አሥረው ወስደው ለጲላጦስ ሰጡት ። ማቴ ፳፯።
ሉቃ ፳፫ ። ዮሐ ፲፰ ።

፪ ወተስእሎ ጲላጦስ ወይቤሎ አንተኑ ንጉሦሙ ለአይ
ሁድ ፡ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ አንተ
ትብል ።
፫ ወአስተዋደይዎ ሊቃነ ካህናት ብዙኃ ፡ ወውእቱሰ
አልቦ ዘአውሥአ ።
፬ ወሐተቶ ካዕበ ጲላጦስ ወይቤሎ አልቦኑ ዘትሰጠው
እንዘ መጠነዝ ያስተዋድዩከ ።
፭ ወኢተሰጥዎ እግዚእ ኢየሱስ ወኢምንተኒ ፡ እስከ
አንከሮ ጲላጦስ ።
፮ ወለለበዓል ያሐዩ ሎሙ አሐደ እምነ ሙቁሓን ዘአ
ብደሩ ።
፯ ወሀሎ አሐዱ ብእሲ ዘስሙ በርባን ሙቁሕ ምስለ
እለ ገብሩ ሀከከ ወምስለ ቀተልተ ነፍስ ።
፰ ወዐርጉ ሕዝብ ወከልሑ ወሰአሉ ይግበር ሎሙ
በከመ ያለምዶ ።
፱ ወአውሥአ ጲላጦስ ወይቤሎሙ ትፈቅዱኑ አሕይዎ
ለክሙ ለንጉሠ አይሁድ ።
፲ እስመ የአምር ከመ በቅንአቶሙ አግብእዎ ሊቃነ
ካህናት ።
፲፩ ወሊቃነ ካህናትሰ ሆከዎሙ ለሕዝብ ከመ በርባንሃ
ይስአሉ ያሕዩ ሎሙ ።
፲፪ ወካዕበ አውሥአ ጲላጦስ ወይቤሎሙ ምንተ እንከ
ትፈቅዱ እረስዮ ለዘተብህለ ንጉሠ አይሁድ ።
፲፫ ወካዕበ ከልሑ ኵሎሙ ወይቤሉ ስቅሎ ።
፲፬ ወይቤሎሙ ጲላጦስ ምንተ እኩየ ገብረ ፡ ወፈድፋደ
ጸርሑ ወይቤሉ ስቅሎ ።
፲፭ ወመከረ ጲላጦስ ይግበር ፈቃዶሙ ለሕዝብ ወአሕ
የወ ሎሙ በርባንሃ ወቀሠፎ ለእግዚእ ኢየሱስ ፡
ወወሀቦሙ ይስቅልዎ ።

## ክፍል ፸ወ፮ ፡ በእንተ ተሣልቆቶሙ ላዕለ እግዚእነ ።

፲፮ ወአብእዎ ሐራ ውሣጤ ዐፀድ ኀበ ምኵናን ወጸ
ውዑ ኵሎ ሠገራተ ሰጲራ ።
፲፯ ወአልበስዎ ሜላተ ወፀፈሩ አክሊለ ዘሦክ ወአስተ
ቀጸልዎ ላዕለ ርእሱ ወተሣለቅዎ ።
፲፰ ወይብልዎ በሐ ንጉሦሙ ለአይሁድ ።
፲፱ ወይኰርዕዎ ርእሶ በሕለት ፡ ወይዌርቅዎ ፡ ወያስተበ
ርኩ ወይሰግዱ ሎቱ ።
፳ ወሶበ ተሣለቁ ላዕሌሁ ሰለብዎ ውእተ ሜላተ ፡ ወአ
ልበስዎ አልባሲሁ ወወሰድዎ ኀበ ይሰቅልዎ ።
፳፩ ወዐበጡ አሐደ እምኃለፍት ስምዖንሃ ቀሬናዌ እት
ወቶ እምሐቅል ወውእቱ አቡሆሙ ለእለ እስክን
ድሮስ ወለሮፎስ ከመ ይፁር መስቀሎ ።
፳፪ ወወሰድዎ ብሔረ ጎልጎታ ዘበትርጓሜሁ ይብልዎ
መካነ ቀራንዮ ።



ጲላጦስም የአይሁድ ንጉሥ አንተ ነህን ? ብሎ ጠየ ፪
ቀው ፡ ጌታ ኢየሱስም መልሶ አንተ ትላለህ አለው ።
የካህናት አለቆችም ብዙ አሳጡት ፡ እሱ ግን የመለ ፫
ሰው ነገር የለም ።
ጲላጦስም ይህን ያህል ሲያሳጡህ አትመልስምን ? ፬
ብሎ እንደገና ጠየቀው ።
ጌታ ኢየሱስም ጲላጦስ እስኪያደንቀው ድረስ ምንም ፭
ምን አልመለሰለትም ። ምዕ ፲፬ ፡ ፷፬ ። ኢሳ ፶፫ ፡ ፯ ።
በበዓል በበዓልም ከእሥረኞች የመረጡትን አንዱን ፮
ይፈታላቸው ነበር ።
ከነፍስ ገዳዮችና ከክፉ አድራጊዎች ጋር የታሠረ ፯
ስሙ በርባን የሚባል አንድ ሰው ነበር ።
ሕዝቡም እንደ ልማዱ ያደርግላቸው ዘንድ እየ ፰
ጮኹ ለመኑ ።
ጲላጦስም መልሶ የአይሁድን ንጉሥ ላድንላችሁ ፱
ትወዳላችሁ ? አላቸው ።
የካህናት አለቆች ቀንተው አሳልፈው እንደ ሰጡት ፲
ያውቃልና ። ዮሐ ፲፩ ፡ ፵፰ ።
የካህናት አለቆች ግን በርባንን እንዲያድንላቸው ፲፩
ይለምኑት ዘንድ ሕዝቡን አነሣሡዋቸው ።
ጲላጦስም እንደገና መልሶ እንግዲህ የአይሁድ ፲፪
ንጉሥ የተባለውን ምን ላድርገው ትወዳላችሁ ?
አላቸው ።
ሁሉም እንደገና ስቀለው እያሉ ጮኹ ። ፲፫
ጲላጦስም ምን ክፉ ሥራ ሠራ ? አላቸው ፡ እነሱ ፲፬
ግን ስቀለው እያሉ በጣም ጮኹ ።
ጲላጣስም የሕዝቡን ፈቃድ ላድርግ አለና በርባንን ፲፭
ፈታላቸው ፡ ጌታ ኢየሱስን ግን ገርፎ ሊሰቅሉት
ሰጣቸው ።

## ክፍል ፸፮ ፡ በጌታችን ላይ ስለ መዘባበታቸው ።

ወታደሮችም ወደ ግቢ ውስጥ ወደ ፍርድ መቀበ ፲፮
ያው አገቡት ፡ ባለወንቹን ጭፍሮች ሁሉ ጠሩ ።
ነጭ ሐርን አለበሱት የእሾህ አክሊል ታትተው ፲፯
በራሱ ላይ ደፉበትና ተዘባበቱበት ።
የአይሁድ ንጉሥ ሰላምታ ይገባሃል ይሉት ነበር ። ፲፰
ራሱን በዘንግ ይመቱት ፡ ይተፉበት ፡ ተንበርክከውም ፲፱
ይሰግዱለት ነበር ።
በተዘባበቱበትም ጊዜ ያንን ነጩን ሐር ገፈፉና ፡ ፳
ልብሱን አልብሰው ወደሚሰቅሉበት ቦታ ወሰዱት ።
መስቀሉንም ይሸከም ዘንድ የቀሬን ሰው የሆነ አንድ ፳፩
ስምዖን የሚባል መንገድ አላፊ ከበረኻ ሲመለስ
ያዙ ፡ እሱም የእለ እስክንድሮስና የሮፎስ አባት
ነው ። ሮሜ ፲፮ ፡ ፲፫ ።
ትርጓሜው የራስ ቅል ወደሚሉት ወደ ጎልጎታ ፳፪
ሥፍራ ወሰዱት ።

፳፫ ወወሀብዎ ይስተዩ ወይነ ምስለ ከርቤ ቱሱሐ፤ ወአ
በየ ሰትየ ።

ክፍል ፸ወ፯ ፤ በእንተ ስቅለቱ ።

፳፬ ወሰቀልዎ ወተዐፀዉ ዲበ አልባሲሁ ወተካፈሉ
ዘከመ ይነሥኡ ።

፳፭ ወሠለስቱ ሰዓት ውእቱ ጊዜ ይሰቅልዎ ።
፳፮ ወይብል መጽሐፈ ጌጋዩ ንጉሦሙ ለአይሁድ ።
፳፯ ወሰቀሉ ምስሌሁ ክልኤተ ፈያተ አሐደ በየማኑ
ወአሐደ በጸጋሙ ።
፳፰ ወተፈጸመ መጽሐፍ ዘይቤ ተኈለቈ ምስለ ገበርተ
ዓመፃ ።
፳፱ ወኃለፍትኒ ይጸርፉ ላዕሌሁ ወየሐውሱ ርእሶሙ
ወይብልዎ፤ አ ዘይነሥቶ ለቤተ፮መቅደስ ወበሠሉስ
ዕለት፤የሐንፆ ።
፴ አድኅን፤ርእሰከ ወረድ፣እመስቀልከ ።
፴፩ ወከማሁ ሊቃነ ካህናትኒ ወጸሐፍት ይሣለቁ ላዕሌሁ
ወይብልዎ ዘበዕደ ያድኅን ወርእሶ ኢይክል አድኅኖ ።

፴፪ ወእመሰ ክርስቶስ ውእቱ ንጉሠ እስራኤል ለይረ
ድኬ እምነ መስቀሉ ንርአይ ወንእመን ቦቱ፤ ወእለሂ
ተሰቅሉ ምስሌሁ ይዘነጕጕዎ ።

ክፍል ፸ወ፰፤ በእንተ ሞቱ በላዕለ መስቀል ።

፴፫ ወሰበ ኮነ ጊዜ ቀትር ጸልመ ፀሐይ ወኵሉ ዓለም
ጸልመ እስከ፡ተሱዐት ሰዓት ።
፴፬ ወጊዜ ተስዐቱ ሰዓት ገዓረ ኢየሱስ በዓቢይ ቃል
ወይቤ፤ኤሎሄ ኤሎሄ ኤልማስ ላማ ሰበቅታኒ፤ዘበት
ርጓሜሁ አምላኪየ አምላኪየ ለምንት ኀደገኒ ።

፴፭ ወበ እለ ይቤሉ እምእለ ይቀውሙ ሀየ ኤልያስሃ
ይጼውዕ ።
፴፮ ወሮጸ አሐዱ ወመልአ ሰፍነገ ብኒአ ወአሰረ በሕለት
ወአስተዮ ወይቤ ኅድጉ ንርአይ ለእመ ይመጽእ
ኤልያስ ያውርዶ ።
፴፯ ወገዓረ እግዚእ ኢየሱስ በዓቢይ ቃል ወመጠወ
ነፍሶ ።
፴፰ ወተሰጠ መንጦላዕተ ምኵራብ ለክልኤ እምላዕሉ
እስከ ታሕቱ ።
፴፱ ወርእዮ ሐራዊ ሊቀ ምእት ዘይቀውም መንጸረ ከመ
ከመዝ ግዒሮ ሞተ ይቤ አማን ዝንቱ ወልደ እግዚ
አብሔር ውእቱ ።
፵ ወሀለዋ አንስት ይቀውማ ወይኔጽራ እምርኁቅ ማር
ያም መግደላዊት፤ ወማርያም እንተ ያዕቆብ ዘይን
እስ፤ ወእሙ ለዮሳ ወሰሎሜ እለ ተለዋሁ እምገሊላ
ወተልእክዎ ።



ከከርቤ ጋር የተቀላቀለ ወይን ሊጠጣ ሰጡት፤ አል ፳፫
ጠጣም አለ ። መዝ ፷፱ ፤ ፳፩ ።

ክፍል ፸፯ ፤ ስለ ስቅለቱ ።

እሱንም ሰቀሉና በልብሶቹ ላይ ዕጣ ተጣጥለው እንደ ፳፬
ድርሻቸው ተካፈሉ ። መዝ ፳፪ ፤ ፲፰ ። ሉቃ ፲፫ ፤ ፴፬ ።
ማቴ ፳፯ ፤ ፴፭ ።
ሲሰቅሉትም ሦስት ሰዓት ነበር ። ፳፭
የበደሉ ደብዳቤም የአይሁድ ንጉሥ ነው ይል ነበር ። ፳፮
ከርሱም ጋር አንዱን በቀኙ አንዱን በግራው ፳፯
ሁለት ወንበዴዎች ሰቀሉ ።
"መጽሐፍ ከዐመፀኞች ጋር ተቈጠረ" ያለው ተፈ ፳፰
ጸመ ። ኢሳ ፶፫ ፤ ፲፪ ።
መንገድ ተላላፊዎችም ይሰድቡት ነበር ፤ ራሳቸውም ፳፱
እየነቀነቁ እንዲህ ይሉት ነበር ፤ አወይ ቤተ መቅደ
ስን አፍርሶ በሦስተኛው ቀን የሚሠራው ! ፲፬ ፤ ፶፰ ።
ራስህን አድን ከመስቀልህም ውረድ ። ፴
እንዲሁም የካህናት አለቆችና ጻፎችም ይዘብቱበ ፴፩
ትና ሌላውን የሚያድን ራሱን ግን ማዳን የማይ
ችል ይሉት ነበር ።
እሱ የእስራኤል ንጉሥ ክርስቶስ ከሆነ እስኪ አሁን ፴፪
ከመስቀሉ ይውረድና አይተን እንመንበት ፤ አብረ
ዉት የተሰቀሉትም ያሽሟጥጡት ነበር ።

ክፍል ፸፰ ፤ በመስቀል ላይ ስለ መሞቱ ።

ቀትርም በሆነ ጊዜ ፀሐይ ጨለመ ፤ ዓለምም ሁሉ ፴፫
እስከ ዘጠኝ ሰዓት ድረስ ጨለማ ሆነ ።
ዘጠኝ ሰዓት በሆነ ጊዜም ጌታ ኢየሱስ በታላቅ ቃል ፴፬
"ኤሎሄ ኤሎሄ ላማ ሰበቅታኒ" ብሎ ጮኸ ፤ ትርጓሜ
ውም "አምላኬ አምላኬ ለምን ተውከኝ" ማለት
ነው ። መዝ ፳፪ ፤ ፩ ።
ከዚያ ቆመው ከነበሩትም ኤልያስን ይጠራል ያሉ ፴፭
አሉ ።
አንዱም ሮጠና በዓይነ በጎ መጻጻውን ሞልቶ በዘ ፴፮
ንግ አሥሮ አጠጣውና ዝም በሉ ኤልያስ መጥቶ
ያወርደው እንደሆነ እንይ ! አለ ።
ጌታ ኢየሱስም በታላቅ ቃል ጮኸ ፤ ነፍሱንም ከሥ ፴፯
ጋው ለየ ።
የምኵራብ መጋረጃም ከላይ እስከ ታች ከሁለት ፴፰
ተቀደደ ።
ፊት ለፊት የቆመው የመቶ አለቃ እንዲህ ጮኸ ፴፱
እንደ ሞተ በየ ጊዜ ፤ ይህ ሰው በእውነት የእግዚአ
ብሔር ልጅ ነው አለ ።
ከሩቅ ቆመው የሚያዩት ሴቶች ነበሩ ከነዚህም ከገ ፵
ሊላ ጀምሮ የተከተሉትና ያገለገሉት ማርያም መግ
ደላዊት ፤ የታናሹ የያዕቆብ እናት ማርያም የዮሳ እና
ትና ሰሎሚ ነበሩ ። ሉቃ ፰ ፤ ፪ - ፳፫ ።

፵፩ ወባዕዳትኒ ብዙኃት እለ ዐርጋ ምስሌሁ ኢየሩ
ሳሌም ።

ክፍል ፸ወ፱ ፡ በእንተ ርደቱ ውስተ መቃብር ።

፵፪ ወመስዮ ዐርብ አሚሃ በአተ ሰንበት ወውእቱ ።

፵፫ መጽአ ዮሴፍ እምአርማትያስ ብእሲ ኄር ወጠቢብ ፡
ወውእቱ ይሴፎ መንግሥተ እግዚአብሔር ወተሀ
በለ ወቦአ ኀበ ጲላጦስ ወሰአለ ሥጋሁ ለእግዚእ
ኢየሱስ ።

፵፬ ወአንከረ ጲላጦስ ወይቤ እፎ ሞተ ወጸውዖ ለሐ
ራዊ ወይቤሎ ወድአኑ ሞተ ፡ ወይቤ እወ ሞተ ።

፵፭ ወአእሚሮ እምኀበ ሐራዊ ከመ ሞተ አዘዘ ይጸግ
ውዎ ለዮሴፍ ሥጋሁ ።

፵፮ ወተሣየጠ ዮሴፍ ሰንዱናተ ወአውረዶ ወገነዞ በሰን
ዱናት ወቀበሮ ውስተ መቃብር ዘአውቀረ ውስተ
ኰኵሕ ።

፵፯ ወማርያም መግደላዊት ወማርያም እንተ ዮሳ ርእያ
ኀበ ቀበርዎ ።

ምዕራፍ ፲ወ፮ ፤

ክፍል ፹ ፡ በእንተ ትንሣኤሁ እሙታን ።

፩ ወሶበ ኀለፈት ሰንበት ማርያም መግደላዊት ወማር
ያም እንተ ያዕቆብ ወሰሎሜ ተሣየጣ አፈወ ከመ
ይምጽኣ ወይቅብኣ ሥጋሁ ።

፪ ወሖራ ወአንግሃ ጥቀ ሐዊረ ኀበ መቃብር በእሑድ
ሰንበት ።

፫ ወሶበ ሠረቀ ፀሐይ ይቤላ በበይናቲሆን መኑ ይከ
ሥታ ለነ ለእብን እምኆኅተ መቃብር ።

፬ ወረዊያን ርእያሃ ለእብን ኀበ አንከርከረት ወዓ
ባይ ይእቲ ጥቀ ።

፭ ወበዊአን ውስተ መቃብር ረከባ ወሬዛ እንዘ ይነብር
መንገለ የማን ወይለብስ አልባሰ ንጹሐ ወደንገፃ ።

፮ ወይቤሎን መልአክ ኢትደንግፃ ኢየሱስሃኑ ናዝራዊ
ዘተሰቅለ ተኃሥሣ ተንሥአ ወኢሀሎ ዝየሰ ወናሁ
መካኑ ኀበ ተቀብረ ።

፯ ወባሕቱ ንግራሆሙ ለአርዳኢሁ ወለጴጥሮስ ከመ
ይቀድሞሙ ገሊላ ወበህየ ይሬእይዎ በከመ ይቤ
ሎሙ ።

፰ ወወፅአ እምነ መቃብር ወጕየ እስመ አኀዞን ረዓድ
ወድንጋፄ ወኢነገራ ወኢለመኑሂ እስመ ፈርሃ ።

፱ ወተንሢኦ በጽባሕ በእሁድ ሰንበት አስተርአየ
ቅድመ ለማርያም መግደላዊት እንተ አምኔሃ አው
ፅአ ሰብዓተ አጋንንተ ።



ከእሱም ጋር ወደ ኢየሩሳሌም የወጡ ብዙዎች ፵፩
ሌሎች ሴቶችም ነበሩ ።

ክፍል ፸፱ ፡ ወደ መቃብር ስለ መውረዱ ።

ያን ጊዜም ዐርብ መሽቶ ለንበት መግባቱ ነበር ። ፵፪
ዮሐ ፲፱ ፡ ፴፰ - ፵፪ ። ሉቃ ፳፫ ፡ ፶ ።
ዮሴፍም ከአርማትያስ መጣ ፡ ሰውዬው ብልህና ደግ ፵፫
ሰው ነበር ፡ እሱም የእግዚአብሔርን መንግሥት ተስፋ
ያደርግ ነበር ፡ ደፍሮ ወደ ጲላጦስ ገባና የጌታ የኢ
የሱስን ሥጋ ለመነ ።
ጲላጦስም እንዴት ሞተ ብሎ አደነቀ ፡ ወታደሩንም ፵፬
ጠርቶ በውኑ ሞተን ? አለው ፡ እሱም አዎን ሞተ
አለው ።
እንደሞተም ከወታደሩ ተረድቶ ሥጋውን ለዮሴፍ ፵፭
እንዲሰጡት አዘዘ ።
ዮሴፍም በፍታ ገዝቶ አውርዶ በበፍታ ገንዞ ከአ ፵፮
ለት በስፈለፈለው አዲስ መቃብር ቀበረው ፡ ደንጊ
ያም አገላብጦ የመቃብሩን አፍ ገጠመ ።
ማርያም መግደላዊትና የዮሳ እናት ማርያም የተቀበ ፵፯
ረበትን ተመለከቱ ።

ምዕራፍ ፲፮ ፤

ክፍል ፹ ፡ ከሙታን ተለይቶ ስለ መነሣቱ ።

ሰንበትም ባለፈች ጊዜ ማርያም መግደላዊት የያዕ ፩
ቆብ እናት ማርያም ሰሎሜ መጥተው ሥጋውን
ሊቀቡ ሽቱ ገዙ ። ማቴ ፳፰ ። ሉቃ ፡ ፳፬ ። ዮሐ ፳ ።
፩ ፡ ቆሮ ፲፭ ።
በመጀመርያው ሰንበትም እጅግ ገሥግሠው ወደ ፪
መቃብር ሄዱ ።
ፀሐይም በወጣ ጊዜ እርስ በርሳቸው ደንጊያውን ፫
ከመቃብሩ አፍ ላይ ማን ያነሣልናል ? አሉ ።
ሮጠውም ደንጊያዪቱን ተነሥታ አዩዋት ፡ እሷም ፬
በጣም ታላቅ ነበረች ።
ወደ መቃብሩም በገቡ ጊዜ አንድ ጐልማሳ ንጹሕ ፭
ልብስ ለብሶ በስተቀኝ ተቀምጦ አዩና ደነገጡ ።
መልአኩም እንዲህ አላቸው ፡ አትደንግጡ የተሰቀለ ፮
ውን የናዝሬቱን ኢየሱስን ትሻላችሁን? ተነሥቷል ፡
ከዚህስ የለም የተቀበረበት ቦታው እነሆ ።
ነገር ግን ሂዱና ለደቀ መዛሙርቱና ለጴጥሮስ ወደ ፯
ገሊላ እንደሚቀድማቸው ንገሯቸው ፡ እንደነገራቸ
ውም በዚያ ያዩታል ። ምዕ ፲፬ ፡ ፳፰ ።
ከመቃብርም ወጥተው ሸሹ ፡ ፍርሃት ድንጋፄም ይዟ ፰
ቸዋልና ስለ ፈሩ ለማንም ለማን አልተናገሩም ።
እሁድ ሰንበት በጥዋት ተነሥቶ ሰባት አጋንንትን ፱
ላወጣላት ለመግደላዊቱ ማርያም ታያት ። ሉቃ
፰ ፡ ፪ ።

### ክፍል ፹ወ፩ ፡ በእንተ አስተርእዮቱ ለብዙኃን ።

፲ ወይእቲ ሐዊራ ዜነወቶሙ ለእለ ምስሌሁ ሀለዉ ቀዲሙ እንዘ ይላህዉ ወይበክዩ ።
፲፩ ወእሙንቱሂ ሰበ ሰምዑ ከመ አስተርአየ ወሕያው ውእቱ ኢአምንዋ ።
፲፪ ወእምዝ አስተርአዮሙ ለክልኤቱ እምኔሆሙ በካልእ ራእይ እንዘ የሐውሩ ሐቅለ ።
፲፫ ወሐሩ እሙንቱሂ ወዜነዉ ለቢጾሙ ፡ ወሎሙኒ ኢአምንዎሙ ።
፲፬ ወእምድኅረዝ ከዐበ እንዘ ይረፍቁ ዐሠርቱ ወአሐዱ አስተርአዮሙ ወገሠፆሙ በእንተ ሕፀተ አሚኖቶሙ ወግዕዘ ጽንዐ ልበሙ እስመ ለእለ ርእይዎ ከመ ተንሥአ ኢአምንዎሙ ።

### ክፍል ፹ወ፪ ፡ በእንተ ፈንዎቱ ሐዋርያተ ።

፲፭ ወይቤሎሙ ሑሩ ውስተ ኵሉ ዓለም ወስብኩ ወንጌለ ለኵሉ ፍጥረት ።
፲፮ ዘአምነ ወዘተጠምቀ ይድኅን ፡ ወዘሰ ኢአምነ ይደየን ።
፲፯ ወዛቲ ተአምር ለእለ አምኑ በስምየ ትተልዎሙ ፡ በስመ ዚአየ አጋንንተ ያወፅኡ ወበካልእ ልሳን ይትናገሩ ሐዲሳተ ።
፲፰ ወአራዊተ ምድር ይእኅዙ በእደዊሆሙ ወእልበ ዘየኃስሞሙ ፡ ወዘሂ ይቀትል ሕምዘ ለእመ በልዑ ወሰትዩ አልቦ ዘይነክዮሙ ፡ ወዲበ ድውያን እደዊሆሙ ያነብሩ ወይሔይዉ ወእሙንቱሂ ይትፌወሱ ።

### ክፍል ፹ወ፫ ፡ በእንተ ዕርገቱ ውስተ ሰማይ ።

፲፱ ወእግዚእነሰ ኢየሱስ እምድኅረ ተናገሮሙ ዐርገ ውስተ ሰማይ ወነበረ በየማነ እግዚአብሔር አቡሁ ።
፳ ወወፂኦሙ እሙንቱ ሰበኩ በኵለሄ ፡ እንዘ እግዚእ ይረድኦ ወቃሎ ያጸንዕ በተአምር ዘይተሉ ።

መልአ ጽሒፈ ብሥራቱ ለማርቆስ ወንጌላዊ ፩ዱ እም ፸ወ፪ቱ አርድእት ።

ወከነ ዘጸሐፎ በሀገረ ሮም በልሳነ አፍርንጊ እምድኅረ ዕርገቱ ለእግዚእነ በሥጋ በ፲ወ፩ ዓመት ፡ ወበ፬ቱ ዓመተ መንግሥቱ ለቀላውዴዎስ ቄሣር ።

ወስብሐት ለእግዚአብሔር ። አሜን ።



### ክፍል ፹፩ ፡ ለብዙዎች ስለ መታየቱ ።

እሷም ሂዳ ቀድሞ ከእሱ ጋር ለነበሩት ሲያዝኑ ፲
ሲያለቅሱ ሳሉ ነገረቻቸው ።
እነሱ ግን እንደተገለጠላትና ሕያው እንደሆነ በሰሙ ፲፩
ጊዜ አላመኗትም ።
ከዚህም በኋላ ከነሱ ለሁለቱ ወደ ሜዳ ሲሄዱ በሌላ ፲፪
አገላለጥ ተገለጠላቸው ። ሉቃ ፳፬ ፡ ፲፫ - ፴፪ ።
እነሱ ደግሞ ሂደው ለባልንጀሮቻቸው ነገሩ ፡ እነሱ ፲፫
ንም ቢሆን አላመኗቸውም ።
ከዚህም በኋላ ደግሞ ዐሥራ አንዱ ለምግብ ተቀም ፲፬
ጠው ሳሉ ተገለጠላቸው ፡ ስለ ሃይማኖታቸው ጉድ
ለት ስለ ልባቸው ጽናት ገሠፃቸው ፡ ያዩትን እንደ
ተነሣ አላመኗቸውምና ።

### ክፍል ፹፪ ፡ ሐዋርያትን ስለ መላኩ ።

ደግሞም እንዲህ አላቸው ፡ ወደ ዓለም ሁሉ ሂዱ ፲፭
ለፍጥረትም ሁሉ ወንጌልን አስተምሩ ። ማቴ ፳፰ ፡
፲፰ - ፲፱ ።
ያመነ የተጠመቀ ይድናል ፡ ያላመነ ግን ይፈረድበ ፲፮
ታል ። ግብ ሐዋ ፪ ፡ ፴፰ ።
ይህቺ ምልክት በስሜ የሚያምኑትን ትከተላቸዋ ፲፯
ለች ፡ በስሜ አጋንንትን ያወጣሉ በሌላ ቋንቋም አዳ
ዲስ ነገርን ይናገራሉ ። ግብ ሐዋ ፪ ፡ ፬ - ፲፩ ። ፲ ፡
፵፮ ። ፲፮ ፡ ፲፯ ።
የምድር አራዊትን በእጃቸው ይይዛሉ የሚጐዳቸ ፲፰
ውም ነገር የለም ፡ የሚገድል መርዝ ቢበሉ ቢጠ
ጡም የሚነካቸው የለም ፡ በድውያን ላይም እጃቸ
ውን ይጭናሉ ይዳሥሣሉ ድውያኑም ይፈወሳሉ ።
ሉቃ ፲ ፡ ፲፱ ። ግብ ሐዋ ፳፰ ፡ ፫ ። ያዕ ፭ ፡ ፲፬ - ፲፭ ።

### ክፍል ፹፫ ፡ ወደ ሰማይ ስለ ማረጉ ።

ጌታ ኢየሱስም ከነጋገራቸው በኋላ ወደ ሰማይ ፲፱
ዐረገ ፡ በአባቱ በእግዚአብሔር ቀኝም ተቀመጠ ።
ግብ ሐዋ ፩ ፡ ፩ - ፲፬ ።
እነሱም ወጥተው ጌታ እያገዘ ፡ ቃሉንም በተከታ ፳
ታይ ትእምርት እያጸናላቸው በአራቱ መዐዝን አስተ
ማሩ ። ዕብ ፪ ፡ ፬ ።

ከሰባ ሁለቱ አርድእት አንዱ ወንጌላዊ ማርቆስ የጻፈው ወንጌል ደረሰ ።

የጻፈውም በሮም አገር በሮማይስጥ ቋንቋ ጌታችን በሥጋ ወደ ሰማይ ባረገ በዐሥራ አንድ ዓመት ፡ ቀላውዴዎስ ቄሣር በነገሠ በአራት ዓመት ነው ።

ለእግዚአብሔር ምስጋና ይሁን ።

## ወንጌል ዘሉቃስ ፩



ወንጌል ቅዱስ ዘእግዚእነ ወመድኃኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ ፡ ዘከመ ጸሐፈ ቅዱስ ሉቃስ ።

ብሥራተ ሉቃስ ወንጌላዊ ፩ዱ እምሮ፪ቱ አርድእት ።

ምዕራፍ ፩ ፤

ክፍል ፩ ፡ በእንተ ጽሒፈ ዜና ።

፩ እስመ ብዙኃን እለ ወጠኑ ይንግሩ ወይምሀሩ በእንተ ግብር ዘአምኑ በላዕሌነ ።

፪ በከመ መሀሩነ እለ ቀደሙነ ርእዮቶ ወተልእክዎ ለቃሉ ።

፫ ወረትዐኒ ሊተኒ እምጥንቱ ወጥዩቀ ኵሎ በበመትልው እጽሕፍ ለከ ኦ አዚዝ ታኦፊላ ።

፬ ከመ ታእምር ጥዩቀ በእንተ ኵሉ ኃይለ ነገር ትምህርተ ዘተመሀርከ ።

ክፍል ፪ ፡ በእንተ ተፈንዎተ መልአክ ኀበ ዘካርያስ ።

፭ ወኮነ በመዋዕለ ሄሮድስ ንጉሠ ይሁዳ ሀሎ አሐዱ ካህን ዘስሙ ዘካርያስ በመዋዕለ አብያ ፡ ወብእሲቱኒ እምአዋልደ አሮን ፡ ወስማ ኤልሳቤጥ ።

፮ ወክልኤሆሙ ጻድቃን እሙንቱ በቅድመ እግዚአብሔር ፡ ወየሐውሩ በኵሉ ትእዛዙ ወሕጉ ወኮነኔሁ ለእግዚአብሔር፡ ወንጹሐን እሙንቱ እምኃጢአት ።

፯ ወበሕቱ አልቦሙ ውሉድ እስመ መካን ይእቲ ኤልሳቤጥ ፡ ወክልኤሆሙ ልሂቃን እሙንቱ ወኃለፈ መዋዕሊሆሙ ።

፰ ወእምዝ አመ ይገብር ግብረ ክህነት በእብሬቱ ቅድመ እግዚአብሔር በከመ ይገብሩ ካህናት ፡ በጽሐ ጊዜ የዐጥን ።

፱ ወቦአ ቤተ መቅደሱ ለእግዚአብሔር ።

፲ ወኵሎሙ ሕዝብ ሀለዉ በምልአሙ ይጼልዩ በአፍአ በጊዜ ሰዓተ ዕጣን ።

፲፩ ወአስተርአዮ መልአከ እግዚአብሔር ቀዊሞ መንገለ የማነ ምሥዋዕ ዘዕጣን ።

፲፪ ወሰበ ርእዮ ደንገፀ ዘካርያስ ፡ ፍርሀት ወረዓድ ወረደ ላዕሌሁ ።

## የሉቃስ ወንጌል ፩

የጌታችን የመድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ቅዱስ ወንጌል ፡ ቅዱስ ሉቃስ እንደ ጻፈው ።

ከሰባ ሁለት አርድእት አንዱ ሉቃስ የጻፈው ወንጌል ይህ ነው ።

ምዕራፍ ፩ ፤

ክፍል ፩ ፡ ወንጌልን ስለ መጻፍ ።

በእኛ ዘንድ ፈጽሞ የታመነውን፤ የሥራውን ነገር ፩
በሥርዓት ሊጽፉና ሊያስተምሩ የጀመሩ ብዙ
ናቸውና ።
ከኛ አስቀድሞ በዓይን ያዩትና ፡ የቃሉ አገልጋዮች ፪
የነበሩ እንዳስተማሩን ። ዮሐ ፩ ፡ ፲፬ ። ፪ ጴጥ ፩ ፡
፩ - ፲፮ ።
የከበርከ ታኦፊላ ሆይ ! እኔም ከጥንት ጀምሬ በእው ፫
ነት ተከትዬዋለሁና ፡ የተረዳሁትን ሁሉ በየተራው
እጽፍልህ ዘንድ ቀናኝ ፤ ግብ ሐዋ ፩ ፡ ፩ ።
ትምህርት አድርገህ የተማርከውን እውነተኛ የወ ፬
ንጌል ቃል ታውቅ ዘንድ ፤ ፩ ጢሞ ፫ ፡ ፲፭ ።

ክፍል ፪ ፡ መልአክ ወደ ዘካርያስ ስለ መላኩ ።

በይሁዳ ንጉሥ በሄሮድስ ዘመን ከአብያ ወገን ፭
ክፍል ዘካርያስ የሚባል አንድ ካህን ነበረ ፡ ሚስ
ቱም ከአሮን ልጆች ወገን ነበረች ፡ ስሟም ኤልሳ
ቤጥ ይባል ነበረ ። ፩ ዜና መዋ ፳፬ ፡ ፲ ።
ሁለቱም በእግዚአብሔር ፊት ጻድቃን ነበሩ ፡ በእግ ፮
ዚአብሔር ትእዛዝ በሕጉና በሥርዓቱ ሁሉ ይሄዱ
ነበሩ ፡ ከኃጢአትም ንጹሐን ነበሩ ። ዘፍ ፲፯ ፡ ፩ ።
ግብ ሐዋ ፳፫ ፡ ፩ ።
ግን ልጅ አልነበራቸውም ፡ ኤልሳቤጥ መካን ነበረ ፯
ችና ሁለቱም አርጅተው ነበር ፡ ዘመናቸውም አልፎ
ነበር ። ዘፍ ፲፰ ፡ ፲፩ ።
ከዚህም በኋላ በእግዚአብሔር ፊት ክህናት እንደሚ ፰
ያደርጉት በተራው የክህነትን ሥራ በሚሠራበት
ጊዜ የሚያጥንበት ጊዜ ደረሰ ።
ወደ እግዚአብሔር ቤተ መቅደስም ገባ ። ዘፀአ ፱
፴ ፡ ፩ - ፰ ።
በዕጣኑ ሰዓት ጊዜም ሕዝቡ በሙሉ በውጭ ቆመው ፲
ይጸልዩ ነበር ። ዘሌዋ ፫ ፡ ፲፮ - ፲፯ ። ግብ ሐዋ ፫ ፩-፲ ።
የእግዚአብሔር መልአክም በዕጣኑ መሠዊያ በስተ ፲፩
ቀኝ በኩል ቆሞ ታየው ። ዘፀአ ፴ ፡ ፩ ።
ዘካርያስም በየው ጊዜ ደነገጠ ፡ ፍርሃት ረዓድ ወረ ፲፪
ደበት ። መሳ ፲፫ ፡ ፮ - ፳ ።

፲፫ ወይቤሎ መልአክ ኢትፍራህ ዘካርያስ እስመ ተሰ
ምዐ ጸሎትከ ቅድመ እግዚአብሔር ፡ ወብእሲትከኒ
ኤልሳቤጥ ትወልድ ለከ ወልደ ወትሰምዮ ስሞ
ዮሐንስ ።
፲፬ ወይከውነከ ትፍሥሕተ ወኃሤተ ወብዙኃን ይትፌ
ሥሑ በልደቱ ።
፲፭ እስመ ዐቢየ ይከውን ውእቱ በቅድመ እግዚአብ
ሔር ወኢይሰቲ ወይነ ወሜሰ ፡ ኢዘያሰክር ወኢ
ዘኢያሰክር ፡ ወይመልእ ላዕሌሁ መንፈስ ቅዱስ እም
ከርሠ እሙ ።
፲፮ ወለብዙኃን እምደቂቀ እስራኤል ይመይጦሙ ኀበ
እግዚአብሔር አምላኮሙ ።
፲፯ ወውእቱ የሐውር ቅድሜሁ በመንፈስ ቅዱስ ወበ
ኃይለ ኤልያስ ፡ ከመ ይሚጥ ልበ አበው ኀበ
ውሉድ ፡ ወሕሊና ከሐድያን ኀበ አእምሮ ጻድቃን ፡
ከመ ይሥራዕ ሕገ ወሕዝበ ዘድልው ለእግዚአ
ብሔር ።

፲፰ ወይቤሎ ዘካርያስ ለመልአከ እግዚአብሔር ፡ በም
ንት አአምር ከመ ይከውን ዝንቱ ኵሉ ፡ ናሁ አነኒ
ልሂቅ ወለብእሲትየኒ ኀለፈ መዋዕሊሃ ።
፲፱ ወተሰጥዎ መልአክ ወይቤሎ ፡ አነ ውእቱ ገብርኤል
ዘእቀውም ቅድመ እግዚአብሔር ፡ ዘተፈኖኩ ኀቤከ
እንግርከ ወእዜኑከ ዘንተ ።

፳ ወናሁ ትከውን በሃመ ወትስእን ነቢበ እስከ አመ
ይከውን ዝንቱ እስመ ኢአመንከኒ ነገርየ ዘይከውን፡
ወይትፌጸም በዕድሜሁ ።
፳፩ ወሀለዉ ሕዝብ ይጼልዩ ወይጸንሕዎ ለዘካርያስ ፡
ወአንከርዎ እስመ ጐንደየ ውስተ ቤተ መቅደስ ።
፳፪ ወወፂአ ኀቤሆሙ አፍአ ስእነ ተናግሮቶሙ ወአእ
መሩ ከመ ዘአስተርአዮ በቤተ መቅደስ ወነበረ
ከማሁ እንዘ በሃም ውእቱ ወይኤምሮሙ በእዴሁ ።

፳፫ ወእምዝ ፈጺሞ መዋዕለ እብሬቱ አተወ ቤቶ ።
፳፬ ወእምድኅረ ክልኤ መዋዕል ፀንሰት ኤልሳቤጥ ብእ
ሲቱ ወከበተት ዕንሳ ኃምስተ አውራኀ ።
፳፭ እንዘ ትብል ከመዝኑ ረሰየኒ ሊተ እግዚአብሔር
አመ ሐውጾ ሐወጸኒ በዝንቱ መዋዕል፡ ያእትት ዝን
ኀጕየ እምሰብእ ።

<u>ክፍል ፫ ፡ በእንተ ብሥራት ።</u>

፳፮ ወበሳድስ ወርኅ ቅፈነወ ገብርኤል መልአክ እምኀበ
እግዚአብሔር ኀበ አሐቲ ሀገር ዘገሊላ እንተ ስማ
ናዝሬት ።
፳፯ ኀበ ድንግል እንተ ተፍኅረት ለብእሲ ዘስሙ ዮሴፍ
ዘእምቤተ ዳዊት ፡ ወስማ ለይእቲ ድንግል ማርያም ።



መልአኩም እንዲህ አለው ዘካርያስ! አትፍራ ጸሎ ፲፫
ትህ በእግዚአብሔር ፊት ተሰምቷልና ሚስትህ ኤል
ሳቤጥም ወንድ ልጅ ትወልድልሃለች ስሙንም ዮሐ
ንስ ትለዋለህ ። ፩ ዮሐ ፫ ፡ ፲፬ ።
ተድላ ደስታ ይሆንልሃል ፡ በመወለዱም ብዙዎች ፲፬
ደስ ይላቸዋል ። ቍ ፷፰ - ፸ ።
እርሱ በእግዚአብሔር ፊት ታላቅ ይሆናልና ፡ የወይ ፲፭
ንና የማር ጠጅ አይጠጣም ፡ የሚያሰክር የማያሰክ
ርም ቢሆን ፡ ከእናቱ ማኅፀን ጀምሮ መንፈስ ቅዱስ
ይመላበታል ። መሳ ፲፫ ፡ ፬ - ፭ ። ማቴ ፲፩ ፡ ፱ - ፲፩ ።
ከእስራኤል ልጆችም ብዙዎቹን ወደ አምላካቸው ፲፮
እግዚአብሔር ይመልሳቸዋል ።
በመንፈስ ቅዱስም በኤልያስም ኃይል በእግዚአብ ፲፯
ሔር ፊት ጸንቶ ይኖራል ፡ ያባቶችን ዕውቀት ወደ
ልጆች ፡ የከሐድያንንም አሳብ ወደ ጻድቃን ዕውቀት
ይመልስ ዘንድ ፡ ሕግን ይሠራ ዘንድ ፡ ሕዝብንም ለእ
ግዚአብሔር የተገባ ያደርግ ዘንድ ። ማቴ ፲፯ ፡ ፲፩ ።
ሚልክ ፫ ፡ ፩ ። ፬ ፡ ፮ ።
ዘካርያስም የእግዚአብሔርን መልአክ እንዲህ ፲፰
አለው ፡ ይህ ሁሉ እንደሚደረግ በምን ዐውቃለሁ?
እነሆ እኔ አርጅቻለሁ ሚስቴም ዘመኗ አልፏልና ።
መልአኩም መልሶ እንዲህ አለው ፡ እኔ በእግዚአብ ፲፱
ሔር ፊት የምቆመው ገብርኤል ነኝ ፡ ይህነንም እነ
ግርህ ዘንድ ወደ አንተ ተልኬአለሁ ። ዳን ፰ ፡ ፲፮ ።
ዕብ ፩ ፡ ፲፬ ።
አሁንም ይህ እስኪሆን ድረስ ድዳ ትሆናለህ መናገር ፳
ይሳንሃል ፡ በጊዜው ሊደረግ ሊፈጸም የነበረውን ነገ
ሬን አላመንከኝምና ። ቍ ፷፫ ።
ሕዝቡ ግን እየጸለዩ ዘካርያስን ይጠብቁት ነበር ፡ አደ ፳፩
ነቁትም በቤተ መቅደስ ውስጥ ዘግይቷልና ።
እነሱ ወደ አሉበት ወደ ውጭ በወጣ ጊዜ እነሱን ፳፪
ማነጋገር ተሳነው ፡ በቤተ መቅደስም የታየው እን
ዳለ አወቁ ፡ እንዲሁም ድዳ ሆኖ በእጁ እያመለከታ
ቸው ኖረ ።
ከዚህም በኋላ ሰሙኑን ጨርሶ ወደ ቤቱ ገባ ። ፳፫
ከሁለት ቀንም በኋላ ሚስቱ ኤልሳቤጥ ፀነሰች ፡ መፅ ፳፬
ነሷንም አምስት ወር ሸሸገች ።
እግዚአብሔር መጐብኘትን በጐበኘኝ ጊዜ በዚህ ፳፭
ወራት ስድቤን ከሰው ያርቅ ዘንድ እንዲህ አደረገ
ልኝ? ብላ ።

<u>ክፍል ፫ ፡ ስለ ብሥራት ።</u>

በስድስተኛውም ወር መልአኩ ገብርኤል ከእግዚአ ፳፮
ብሔር ዘንድ ከገሊላ አገር ወደ አንዲት ናዝሬት
ወደምትባለው ተላከ ። ዮሐ ፩ ፡ ፵፮ ።
ከዳዊት ወገን ለሚሆን ዮሴፍ ለሚባል ሰው ወደ ፳፯
ታጨችው አንዲት ብላቴና የዚያች ድንግል ስሟ
ማርያም ይባል ነበረ ። ማቴ ፩ ፡ ፲፮ - ፲፰ ።

፳፰ ወቦአ መልአክ ኀቤሃ ወይቤላ ፡ ተፈሥሒ ፍሥሕት
አ ምልእተ ጸጋ እግዚአብሔር ምስሌኪ ፡ ቡርክት
አንቲ እምአንስት ።
፳፱ ወርእያ ደንገፀት እምቃሉ ወሐለየት ወትቤ ፡ እፎኑ
እንጋ ዘከመዝ አምኃ ይትአምኁ ።
፴ ወይቤላ መልአክ ኢትፍርሂ ማርያም እስመ ረከብኪ
ሞገሰ በኀበ እግዚአብሔር ።

፴፩ ወናሁ ትፀንሲ ወትወልዲ ወልደ ወትሰምዪዮ ስሞ
ኢየሱስ ።

፴፪ ውእቱ ዓቢይ ወይሰመይ ወልደ እግዚአብሔር
ልዑል ፡ ወይሁቦ እግዚአብሔር አምላክ መንበረ
ዳዊት አቡሁ ።
፴፫ ወይነግሥ ለቤተ ያዕቆብ ለዓለም ወአልቦ ማኅለቅት
ለመንግሥቱ ።
፴፬ ወትቤሎ ማርያም ለመልአክ እፎኑ ይከውነኒ ዝንቱ
እንዘ ኢየአምር ብእሴ ።
፴፭ ወአውሥአ መልአክ ወይቤላ መንፈሰ እግዚአብሔር
ቅዱስ ይመጽእ ላዕሌኪ ወኃይለ ልዑል ይጼልለኪ ፡
ወዘኒ ይትወለድ እምኔኪ ቅዱስ ውእቱ ወይሰመይ
ወልደ እግዚአብሔር ልዑል ።

፴፮ ወናሁ ኤልሳቤጥኒ እንተ እምአዝማድኪ ይእቲኒ
ፀንሰት ወረከበት ወልደ በልህቃቲሃ ወብርስዓቲሃ ፡
ወናሁ ሳድስ ዝንቱ ወርኅ ለእንተ ይብልዋ መከን ።
፴፯ እስመ አልቦ ነገር ዘይሰአኖ ለእግዚአብሔር ።

፴፰ ወትቤሎ ማርያም ለመልአክ ነየ አመቱ ለእግዚአብ
ሔር ይኩነኒ በከመ ትቤለኒ ፡ ወእምዝ ሖረ ወኃለፈ
እምኀቤሃ መልአክ ።

<u>ክፍል ፬ ፡ በእንተ ሑረታ ለማርያም ኀበ ኤልሳቤጥ ።</u>

፴፱ ወተንሥአት ማርያም ፍጡነ በውእቱ መዋዕል ፡
ወሖረት ደወለ ዓይነ ክርም ወበጽሐት ሀገረ ዳዊት
ዘይሁዳ ።
፵ ወቦአት ቤተ ዘካርያስ ወአምኃታ ለኤልሳቤጥ ።

፵፩ ወሶበ ሰምዐት ኤልሳቤጥ ቃላ ለማርያም እንዘ ትት
አምኃ አንፈርዐጸ እጓል በውስተ ከርሣ ፡ ወመልአ
መንፈስ ቅዱስ ላዕለ ኤልሳቤጥ ።
፵፪ ወከልሐት በዓቢይ ቃል ወትቤ ቡርክት አንቲ እም
አንስት ወቡሩክ ፍሬ ከርሥኪ ።

፵፫ ወምንትኑ አነ ከመ ትምጽኢ ኀቤየ እሙ ለእግዚእየ ።



መልአኩም ወደሷ ገብቶ ደስ ይበልሽ ፡ ጸጋን የተ ፳፰
መላሽ ሆይ! እግዚአብሔር ካንቺ ጋር ነው ፡ አንቺም
ከሴቶች ተለይተሽ የተባረክሽ ነሽ ። ዮሐ ፡ ፩ ፡ ፲፯ ።
አይታም ከነጋገሩ የተነሣ ደነገጠች ፡ እንዴት እንዲህ ፳፱
ያለ ሰላምታ ይቀበሏልን? ብላ አሰበች ።
መልአኩም እንዲህ አላት ማርያም ! አትፍሪ ፡ በእ ፴
ግዚአብሔር ዘንድ ባለሟልነትን አግኝተሻልና ።
ግብ ሐዋ ፯ ፡ ፵፯ ።
እነሆ ትፀንሺያለሽ ወንድ ልጅም ትወልጂያለሽ ፡ ፴፩
ስሙንም ኢየሱስ ትዪዋለሽ ። ኢሳ ፯ ፡ ፲፬ ። ማቴ
፩ ፡ ፳፩ - ፳፫ ።
እሱ ታላቅ ነው ፤ የልዑል እግዚአብሔር ልጅ ይባ ፴፪
ላል ፡ እግዚአብሔር አምላክም የአባቱን የዳዊትን
ዙፋን ይሰጠዋል ። ፪ ሳሙ ፯ ፡ ፲፪ ።
ለያዕቆብ ወገንም ለዘላለሙ ነግሦ ይኖራል ፡ ለመን ፴፫
ግሥቱም ፍጻሜ የለውም ። ዳን ፯ ፡ ፲፬ ። ሚክ ፬ ፡ ፯ ።
ማርያም መልአኩን ወንድ ሳላውቅ ይህ እንዴት ፴፬
ይሆንልኛል ? አለችው ።
መልአኩም መልሶ እንዲህ አላት ፡ የቅዱስ እግዚአ ፴፭
ብሔር መንፈስ ያድርብሻል የልዑል ኀይል ይጋር
ድሻል ፡ ካንቺ የሚወለደውም ቅዱስ ነው ፡ የልዑል
እግዚአብሔር ልጅ ይባላል ። ማቴ ፩ ፡ ፲፰ - ፳ ።
ዳን ፱ ፡ ፳፬ ።
ከዘመዶችስ ወገን የምትሆን ኤልሳቤጥም እነሆ እሷ ፴፮
በእርጅናዋ ወራት ፀነሰች ፡ ወንድ ልጅንም አገኘች ፡
መኻን ለሚሏትም ይህ ወር ስድስተኛ ወሯ ነው ።
ለእግዚአብሔር የሚሳነው ነገር የለምና ፡ ኤር ፴፪ ፡ ፴፯
፲፯ - ፳፯ ። ዘካ ፰ ፡ ፯ ። ሮሜ ፬ ፡ ፳፩ ።
ማርያምም መልአኩን እነሆ የእግዚአብሔር ገረዱ ፴፰
አለሁ ፡ እንዳልክ ይሁንልኝ አለችው ፡ ከዚህ በኋላ
መልአኩ ከሷ አልፎ ሄደ ።

<u>ክፍል ፬ ፡ ማርያም ወደ ኤልሳቤጥ ስለ መሄዷ ።</u>

በዚያ ወራት ማርያም ፈጥና ተነሣችና የክረምት ፴፱
ምንጭ በሚበዛበት በደጋው ሄደች የይሁዳ ዕፃ ወደ
ምትሆን ወደ ዳዊት አገር ደረሰች ።
ወደ ዘካርያስ ቤትም ገብታ ኤልሳቤጥን እንዴት ፵
ነሽ? አለቻት ።
ኤልሳቤጥም እንዴት ነሽ ስትላት የማርያምን ቃል ፵፩
በሰማች ጊዜ ፅንሱ በማኅፀኗ ውስጥ በደስታ ዘለለ ፡
በኤልሳቤጥም መንፈስ ቅዱስ መላበት ። ቊ ፡ ፲፭ ።
በታላቅ ቃልም ጮኽ እንዲህ አለች ከሴቶች ተለይ ፵፪
ተሽ አንቺ የተባረክሽ ነሽ ፡ የማኅፀንሽ ፍሬም
ቡሩክ ነው ። ቊ ፳፰ ።
የጌታዬ እናት! ወደ እኔ ትመጪ ዘንድ እኔ ምን ፵፫
ድር ነኝ ?

፵፬ እስመ ናሁ ሰበ ሰማዕኩ ቃለኪ እንዘ ትትአምኀኒ
አንፈርዐጸ እጓል በውስተ ከርሥየ በፍሥሐ ወበ
ኃሤት ።
፵፭ ወብፅዕት አንቲ እንተ ተአምኒ ከመ ይከውን ቃል
ዘነገሩኪ እምኀበ እግዚአብሔር ።
፵፮ ወትቤ ማርያም ታዐብዮ ነፍስየ ለእግዚአብሔር ።
፵፯ ወትትኄሠይ መንፈስየ በአምላኪየ ወመድኃኒየ ።
፵፰ እስመ ርእየ ሕማማ ለአመቱ ፥ ናሁ እምይእዜሰ ያስ
ተበፅዑኒ ኵሉ ትውልድ ።
፵፱ እስመ ገብረ ሊተ ኀይለ ዓቢያተ ወቅዱስ ስሙ ።
፶ ወሣህሉኒ ለትውልደ ትውልድ ለእለ ይፈርህዎ ።
፶፩ ወገብረ ኀይለ በመዝራዕቱ ፡ ወዘረዎሙ ለእለ ያዐ
ብዩ ሕሊና ልቦሙ ።
፶፪ ወነሠቶሙ ለኃያላን እመናብርቲሆሙ ፡ አዕበዮሙ
ለትሑታን ።
፶፫ ወአጽገቦሙ እምበረከቱ ለርኁባን ፥ ወፈነዎሙ ዕራ
ቆሙ ለብዑላን ።
፶፬ ወተወክፎ ለእስራኤል ቍልዔሁ ፥ ወተዘከረ ሣህሎ ።
፶፭ ዘይቤሎሙ ለአበዊነ ለአብርሃም ወለዘርኡ እስከ
ለዓለም ።
፶፮ ወነበረት ማርያም ኀቤሃ መጠነ ሠለስቱ አውራኀ ፥
ወእምድኅሬሁ አተወት ቤታ ።

<u>ክፍል ፫ ፥ በእንተ ልደተ ዮሐንስ መጥምቅ ።</u>

፶፯ ወበጽሐ ወርኃ ለኤልሳቤጥ ከመ ትለድ ፥ ወወለደት
ወልደ ።
፶፰ ወሰበ ሰምዑ አዝማዲሃ ወአግዋሪሃ ከመ አዕበየ
እግዚአብሔር ሣህሎ ላዕሌሃ ፥ ተፈሥሑ ላቲ ።
፶፱ ወእምዝ አመ ሰሙን ዕለት መጽኡ ከመ ይግዝርዎ
ለሕፃን ወሰመይዎ በስመ አቡሁ ዘካርያስ ።
፷ ወአውሥአት እሙ ወትቤ አልቦ ፥ አላ ዮሐንስ
ይሰመይ ።
፷፩ ወይቤልዋ አልቦ እምአዝማድኪ ዘከማሁ ስሙ ።
፷፪ ወቀጸብዎ ለአቡሁ ወይቤልዎ መነ ትፈቅድ ይሰ
ምይዎ ።
፷፫ ወሰአለ ለውሀ ወጸሐፈ እንዘ ይብል ዮሐንስ ይሰ
መይ ስሙ ፥ ወአንከሩ ኵሎሙ ።
፷፬ ወተከሥተ አፉሁ ሶቤሃ ወልሳኑ ነበበ ፡ ወባረከ ለእግ
ዚአብሔር ።

እነሆም የሰላምታሽ ድምፅ በሰማሁ ጊዜ ፥ ልጁ በማ ፵፬
ኅፀኔ በፍጹም ደስታ ዘሏልና ።
ከእግዚአብሔር ተልከው የነገሩሽ ቃል እንደሚደረግ ፵፭
የምታምኚ አንቺ ንእድ ክብርት ነሽ ። ምዕ ፲፩ ፥ ፳፰ ።
ማርያም እንዲህ አለች ፥ ሰውነቴ እግዚአብሔርን ታከ ፵፮
ብረዋለች ። ፩ ሳሙ ፪ ፡ ፩ - ፲ ።
ልቡናዬ በፈጣሪዬ በመድኃኒቴ ደስ ይላታል ። ፵፯
ዕንባ ፫ ፥ ፲፰ ።
የአገልጋይቱን መከራ አይቷልና ፥ እነሆ ከዛሬ ጀምሮ ፵፰
ትውልድ ሁሉ ብፅዕት ይሉኛል ። መዝ ፻፲፫ ፥ ፯ - ፯ ።
ዘፍ ፴ ፥ ፲፫ ። ምዕ ፲፩ ፥ ፳፯ ።
ታላላቅ ሥራ ሠርቶልኛል ፥ ስሙም ቅዱስ ነው ። መዝ ፵፱
፻፳፯ ፥ ፫ ። ኢሳ ፯ ፥ ፫ ።
ይቅርታውም ፥ ለሚፈሩት ለልጅ ልጅ ነው ። መዝ ፶
፻፫ ፥ ፲፫ - ፲፯ ።
በሥልጣኑ ኀይልን አደረገ ፥ የልቡናቸውን አሳብ ከፍ ፶፩
ከፍ የሚያደርጉትንም በተናቸው ። ፪ ሳሙ ፳፪ ፥ ፳፰
ኃያላኑን ከመዓርጋቸው አዋረዳቸው ፥ የተዋረዱትን ፶፪
ከፍ ከፍ አደረጋቸው ። መዝ ፻፵፯ ፥ ፮ ።
የተራቡትን ከበረከቱ አጠገባቸው ፥ ባለጸጎችን ባዶ ፶፫
እጃቸውን ሰደዳቸው ። መዝ ፴፫ ፥ ፲፩ ። መዝ ፻፯ ፥
፱ ። ዮሐ ፩ ፥ ፲፩ ።
ባርያውን እስራኤልን ተቀበለው ፥ ይቅርታውንም ፶፬
አሰበ ። ዘዳግ ፯ ፥ ፯ - ፲ ።
ለአባቶቻችን ለአብርሃምና ለዘሩ እስከ ዘላለም ፶፭
አደርገዋለሁ ያለውን ። ዘፍጥ ፲፯ ፥ ፯ ። ፲፰ ፥ ፲፰ ።
ማርያም ሦስት ወር ያህል ከርሷ ዘንድ ተቀምጣ ፶፮
ከዚህ በኋላ ወደ ቤቷ ተመለሰች ።

<u>ክፍል ፫ ፥ ስለ መጥምቁ ዮሐንስ ልደት ።</u>

ኤልሳቤጥም ልትወልድ ቀኗ ደረሰ ፥ ወንድ ልጅም ፶፯
ወለደች ። ቍ ፥ ፲፫ ።
ዘመዶቿና ጎረቤቶቿ እግዚአብሔር ቸርነቱ እንዳበ ፶፰
ዛላት በሰሙ ጊዜ ፥ በእሷ ደስ አላቸው ።
ከዚህም በኋላ በስምንተኛው ቀን ሕፃኑን ሊገዝሩት ፶፱
መጡ ፥ በአባቱ ስምም ዘካርያስ ብለው ጠሩት ። ዘፍ
፲፯ ፥ ፲፪ ።
እናቱ ግን መልሳ አይሆንም ፥ ዮሐንስ ይባል ፥ አለች ። ፷
ቍ ፥ ፫ ።
ከዘመዶችሽ ስሙ እንዲህ የሚባል የለም ። ፷፩
አባቱንም ጠቅሰው ማን ሊባል ትወዳለህ ? አሉት ። ፷፪
ብራናም ለምኖ ስሙ ዮሐንስ ይባል ብሎ ጻፈ ፥ ፷፫
ሁሉም አደነቁ ።
ያን ጊዜም አንደበቱ ተከፍቶ ምላሱ ረትቶ ተናገረ ፡ ፷፬
እግዚአብሔርንም አመሰገነ ። መዝ ፻፲፯ ፥ ፳ ።

፷፭ ወኮነ ፍርሃት ላዕለ ኵሉ ሰብእ ዘውእቱ ብሔር፡
ወላዕለ ኵሉ ደወለ ይሁዳ፡ ወተናገርዎ ለዝንቱ ነገር
በኵሉ ብሔረ ይሁዳ ።
፷፮ ወዐቀብዎ በልቦሙ ኵሎሙ እለ ሰምዕዎ ወይቤሉ
ምንትኑ እንጋ ይከውን እምዝንቱ ሕፃን፡ እስመ
እደ እግዚአብሔር ላዕሌሁ ።
፷፯ ወመልአ መንፈስ ቅዱስ ላዕለ ዘካርያስ አቡሁ ወተ
ነበየ ወይቤ ።
፷፰ ይትባረክ እግዚአብሔር አምላከ እስራኤል ዘተሣሀ
ለነ ወገብረ መድኃኒተ ለሕዝበ ዚአሁ ።
፷፱ አንሥአ ለነ ቀርነ መድኃኒትነ እምቤተ ዳዊት ገብሩ ።
፸ በከመ ነበበ በአፈ ነቢያቲሁ ቅዱሳን እለ እምዓለም ።
፸፩ ከመ ያድኅነነ እምእደ ፀርነ ወእምእደ ኵሎሙ እለ
ይጸልኡነ ።
፸፪ ከመ ይግበር ሣህሎ ምስለ አበዊነ ወከመ ይዘከር
ኪዳኖ ቅዱሰ ።
፸፫ መሐላሁ ዘመሐለ ለአብርሃም አቡነ ።
፸፬ ከመ የሀበነ በዘኢንፈርሀ እምእደ ፀርነ ።
፸፭ ያድኅነነ ናምልኮ በጽድቅ ወበርትዕ በቅድሜሁ ወበ
ኵሉ መዋዕሊነ ።
፸፮ ወአንተኒ ሕፃን ነቢየ ልዑል ትሰመይ እስመ ተሐ
ውር ቅድመ እግዚአብሔር ከመ ትጺሕ ፍኖቶ ።
፸፯ ከመ ተሀበሙ ለአሕዛብ ያእምሩ መድኃኒቶሙ በዘ
ይትኀደግ ሎሙ ኃጢአቶሙ ።
፸፰ በሣህሉ ወበምሕረቱ ለአምላክነ ለዘሐወፀነ እምአር
ያም ።
፸፱ ወሠረቀ ከመ ያርእዮሙ ብርሃኖ ለእለ ይነብሩ ውስተ
ጽልመት ወጽላሎተ ሞት፡ ከመ ያርትዕ እገሪነ ውስተ
ፍኖተ ሰላም ።
፹ ወልሀቀ ሕፃን ወጸንዐ በኃይለ መንፈስ ቅዱስ ወነበረ
ሐቅለ፡ እስከ አመ ያገይሥዎ ኀበ እስራኤል ።

በዚያ አገር ሰው ሁሉ ላይ በይሁዳም አውራጃ ሁሉ ፷፭
ላይ ፍርሃት ሆነ፡ ይህንንም በይሁዳ አውራጃ ሁሉ
አወሩት ። መዝ ፻፬ ፡ ፫ - ፬ ።
የሰሙትም ሁሉ በልባቸው አስተዋሉትና ከዚህ ፷፮
ልጅ ምን ይደረግ ይሆን? እንጃ፡ የእግዚአብሔር
እጅ በላዩ ናትና አሉ ። ዕዝ ፯ ፡ ፯ ። ሉቃ ፷ ፡ ፲፭ ።
በአባቱ በዘካርያስም መንፈስ ቅዱስ መላበትና እን ፷፯
ዲህ ብሎ ተነበየ ።
"ይቅር ያለን ለወገኖቹ ድኅነትን ያደረገ የእስራኤል ፷፰
አምላክ እግዚአብሔር ይክበር ይመስገን" ። መዝ
፺፩ ፡ ፲፫ ። ኢሳ ፺፫ ፡ ፩ ። ሉቃ ፯ ፡ ፲፯ ።
ከአገልጋዩ ከዳዊት ቤት የምንድንበትን ቀንድ አነ ፷፱
ሣልን ። መዝ ፻፴፪ ፡ ፲፯ ። ግብ ሐዋ ፬ ፡ ፲፪ ።
ከጥንት በነበሩ በነቢያቱ እንደበት እንደተናገረ ። ፸
ኤር ፳፫ ፡ ፮ ። ግብ ሐዋ ፫ ፡ ፳፩ - ፳፬ ።
ከጠላቶቻችን እጅ ከሚጠሉንም ሁሉ ያድነን ዘንድ ። ፸፩
መዝ ፻፮ ፡ ፲ ። ዘሌ ፳፮ ፡ ፵፪ ።
ቸርነቱን ከአባቶቻችን ጋር ያደርግ ዘንድ የተቀደሰ ፸፪
ኪዳኑንም ያስብ ዘንድ ። ዘፍ ፳፪ ፡ ፲፮ ። ሚክ ፯ ፡ ፳ ።
ኤር ፴፩ ፡ ፴፫ ።
ለአባታችን ለአብርሃም የማለውን መሐላ ያስብ ፸፫
ዘንድ ።
ከጠላቶቻችን እጅ የማንፈራበት ረድኤቱን ይሰጠን ፸፬
ዘንድ ። ቲቶ ፪ ፡ ፲፪ - ፲፬ ።
ሊያድነንም በፊቱ በዘመናችን ሁሉ በእውነት በቅ ፸፭
ንነት እናመልከው ዘንድ ። ገላ ፪ ፡ ፳ ። ቆላ ፩ ፡ ፳፩ ።
አንተም ልጅ የልዑል ነቢይ ትባላለህ፡ መንገዱን ፸፮
ትጠርግ ዘንድ በፊቱ ትሄዳለህና ። ቍ ፲፯ ። ማቴ
፫ ፡ ፫ ። ሚልክ ፬ ፡ ፭ ።
ኃጢአታቸው በሚሠረይላቸው ገንዘብ መድኃኒታ ፸፯
ቸውን እንዲያውቁ አሕዛብን ታስተምራቸው ዘንድ ።
ኢሳ ፶፫ ፡ ፲፩ ። ኤር ፴፩ ፡ ፴፬ ።
ከአርያም በጐበኘን በአምላካችን በይቅርታውና ፸፰
በቸርነቱ ። ዘኍል ፳፬ ፡ ፲፯ ። ኢሳ ፷፩ ፡ ፪ ።
በጨለማና በሞት ጥላ ለነበሩት ብርሃኑን ያሳያቸው ፸፱
ዘንድ እግራችንንም ወደ ሰላም ጐዳና ያቀና ዘንድ ።
ኢሳ ፱ ፡ ፪ ። ፷ ፡ ፳ ። ሚል ፬ ፡ ፪ ። ሮሜ ፫ ፡ ፲፯ ።
ሕፃኑም አደገ፡ በመንፈስ ቅዱስም ኃይል ጸና፡ ለእ ፹
ስራኤልም እስከ ተገለጠበት ድረስ፡ በምድረ በዳ
ኖረ ። ምዕ ፪ ፡ ፵ - ፶፪ ። ማቴ ፫ ፡ ፩ ።

ምዕራፍ ፪ ፤

ክፍል ፯ ፡ በእንተ ጽሕፈተ ሕዝብ ።

፩ ወኮነ በውእቱ መዋዕል ወፅአ ትእዛዝ እምኀበ አው
ግስጦስ ቄሣር ከመ ይጸሐፍ ኵሉ ዓለም ።
፪ ወውእቱ ጻሕፍ ቀዳሚ አመ ቄሬኔዎስ መስፍን
ለሶርያ ።

ምዕራፍ ፪ ፤

ክፍል ፯ ፡ ስለ ሕዝብ ቈጠራ ።

በዚያ ወራት እንዲህ ሆነ፡ ሕዝቡ ሁሉ ይቈጠር ፩
ዘንድ ከአውግስጦስ ቄሣር ትእዛዝ ወጣ ።
ቄሬኔዎስም ለሶርያ መስፍን በነበረ ጊዜ ይህ መጀ ፪
መርያ ቈጠራ ነበር ። ግብ ሐዋ ፭ ፡ ፴፯ ።

## ወንጌል ዘሉቃስ ፪ ።

፫ ወሐረ ኵሉ ሰብእ ይጸሐፍ በበሀገሩ ።
፬ ወዐርገ ዮሴፍኒ እምገሊላ እምሀገረ ናዝሬት መንገለ
ይሁዳ ኀበ ሀገረ ዳዊት እንተ ስማ ቤተ ልሔም
እስመ እምቤተ ዳዊት ወእምአዝማደ ቤቱ ውእቱ ።

፭ ወሐረ ይጸሐፍ ምስለ ማርያም እንተ ፈኀሩ ሎቱ
እንዘ ፅንስት ይእቲ ።

ክፍል ፪ ፡ በእንተ ልደተ እግዚእነ ።

፮ ወእምዝ እንዘ ሀለዉ ህየ በጽሐ ዕለተ ወሊዶታ ።
፯ ወወለደት ወልደ ዘበኵራ ወአሰረቶ መንኰብያቲሁ
ወአስከበቶ ውስተ ጎል ወጠብለለቶ በአጽርቅት
እስመ አልቦሙ መከን ውስተ ማኅደሮሙ ።
፰ ወሀለዉ ኖሎት ውስተ ውእቱ ብሔር ይተግሁ ወይ
ሔልዉ ወየዐቅቡ መራዕይሆሙ ሌሊተ በበእብሬ
ቶሙ ።
፱ ወናሁ ቆመ መልአከ እግዚአብሔር ኀቤሆሙ ወስብ
ሐተ እግዚአብሔር ሠረቀ ላዕሌሆሙ ወፈርሁ ዐቢየ
ፍርሃተ ።
፲ ወይቤሎሙ መልአክ ኢትፍርሁ እስመ ናሁ እዜን
ወክሙ ዓቢየ ዜና ፍሥሐ ዘይከውን ለክሙ ወለ
ኵሉ ዓለም ።
፲፩ እስመ ናሁ ተወልደ ለክሙ ዮም መድኅን ዘውእቱ
ክርስቶስ እግዚእ ቡሩክ በሀገረ ዳዊት ።
፲፪ ወከመዝ ትእምርቱ ለክሙ ትረክቡ ሕፃነ እሡረ
መንኰብያቲሁ ወጥብሉለ በአፅርቅት ወስኩበ
ውስተ ጎል ።
፲፫ ወግብተ መጽኡ ምስለ ውእቱ መልአክ ብዙኃን
ሐራ ሰማይ እንዘ ይሴብሕዎ ለእግዚአብሔር ።

፲፬ ወይብሉ ስብሐት ለእግዚአብሔር በሰማያት ፡ ወሰ
ላም በምድር ለእጓለ እመሕያው ሥምረቱ ።

፲፭ ወእምዝ ዐረጎሙ መላእክት እምኀቤሆሙ ውስተ
ሰማይ ይቤሉ እሙንቱ ሰብእ ኖሎት በበይናቲሆሙ
ንሑር እስከ ቤተ ልሔም ወናእምር ዘንተ ነገረ
ዘአርአየነ እግዚአብሔር ።
፲፮ ወሐሩ ፍጡነ ወረከብዎሙ ለማርያም ወለዮሴፍ ወለ
ሕፃንኒ ይሰክብ ውስተ ጎል ።
፲፯ ወርእዮሙ አእመሩ ከመ በእንተ ውእቱ ሕፃን ዘነገ
ርዎሙ ።
፲፰ ወአንከሩ ኵሎሙ እለ ሰምዑ ዘነገርዎሙ ኖሎት ።
፲፱ ወማርያምሰ ተዐቅብ ዘንተ ኵሎ ነገረ ወትወድዮ
ውስተ ልባ ።
፳ ወተመይጡ ኖሎት እንዘ ይሴብሕዎ ወየአኵትዎ ለእ
ግዚአብሔር በእንተ ኵሉ ዘርእዩ ወሰምዑ ዘከመ
ይቤልዎሙ ።

## የሉቃስ ወንጌል ፪ ።

ሰው ሁሉ ሊቈጠር በያገሩ ሄደ ። ፫
ዮሴፍም ከገሊላ ከናዝሬት ከተማ ተነሥቶ ቤተ ፬
ልሄም ወደምትባለው ወደ ዳዊት ከተማ ወደ
ይሁዳ ሄደ ፡ እሱ ከዳዊት ወገን ከዘመዶቹም ነውና ።
ምዕ ፩ ፡ ፳፯ ። ሚክ ፭ ፡ ፪ ።
ፀንሳ ሳለች ከጨለት ከማርያም ጋር ሊጻፍ ሄደ ። ፭
ምዕ ፩ ፡ ፳፯ ።

ክፍል ፪ ፡ ስለ ጌታችን መወለድ ።

ከዚህም በኋላ ከዚያ ሳሉ የምትወልድበት ቀን ደረሰ ። ፮
የበኵር ልጅዋንም ወለደች ፡ አውራ ጣቱንም አሰረ ፯
ቺው ፡ በጨርቅም ጠቅልላ በበረት አስተኛችው ፡
በማደሪያቸው በታ አልነበራቸውምና ። ማቴ ፩ ፡ ፳፭ ።
በዚያ መንደር እረኞች ነበሩ ፡ ሌሊቱንም በየፈንታ ፰
ቸው ተግተው መንጋቸውን ይጠብቁ ነበር ።

እነሆ የእግዚአብሔር መልአክ አጠገባቸው ቆመ ፡ ፱
የእግዚአብሔርም ብርሃን በላያቸው ላይ በራ ፡ ታላቅ
ፍርሃትንም ፈሩ ። ኢሳ ፰ ፡ ፮ ።
መልአኩም እነሆ ለእናንተና ለመላው ዓለም ደስታ ፲
የሚሆን ታላቅ የምሥራች እነግራችኋለሁና አትፍሩ
አላቸው ። ኢሳ ፰ ፡ ፩ - ፫ ።
እነሆ ዛሬ በዳዊት አገር መድኅን ፡ እርሱም ክርስቶስ ፲፩
ጌታ የሆነ ተወልዶላችኋልና ። ዮሐ ፬ ፡ ፳፭ ።
ለእናንተም ምልክቱ እንዲህ ነው ፡ ሕፃኑ አውራ ፲፪
ጣቱን ታሥሮ ፡ በጨርቅ ተጠቅልሎ ፡ በበረት ውስጥ
ተኝቶ ታገኙታላችሁ ።
ድንገትም ከዚያ መልአክ ጋር ብዙ የሰማይ ሠራዊት ፲፫
እግዚአብሔርን እያመሰገኑ መጡ ። ዳን ፯ ፡ ፲ ። ራእ
ዮሐ ፭ ፡ ፲፩ ።
በሰማይ ለእግዚአብሔር ምስጋና ይሁን ፡ በምድርም ፲፬
ሰላም ለሰው ልጅ በጎ ፈቃድ እያሉ ። ኢሳ ፶፯ ፡
፲፱ ። ሮሜ ፭ ፡ ፩ ። ኤፌ ፪ ፡ ፲፬ - ፲፯ ።
ከዚህም በኋላ መላእክት ከእነሱ ዘንድ ወደ ሰማይ ፲፭
በረጉ ጊዜ ፡ እነዚያ እረኞች ሰዎች እርስ በርሳቸው
ኑ ወደ ቤተ ልሄም ሂደን ይህን እግዚአብሔር የገለ
ጠልንን ነገር እንወቅ አሉ ።
ፈጥነውም ሄዱና ማርያምንና ዮሴፍን ሕፃኑንም በበ ፲፮
ረት ውስጥ ተኝቶ አገኟቸው ። ማቴ ፪ ፡ ፲፩ ።
አይተውም የነገሯቸው ስለዚህ ሕፃን እንደሆነ ፡ ፲፯
ዐወቁ ። ቈ ፲ - ፲፪ ።
እረኞች የነገሯቸውን የሰሙ ሁሉ አደነቁ ። ፲፰
ማርያም ግን ይህን ሁሉ ነገር ታስተውለው ፡ በል ፲፱
ቧም ታኖረው ነበር ። ምዕ ፩ ፡ ፳፱ ። ፴፰ - ፵፰ ።
እረኞችም ፡ መላእክት እንደነገሯቸው በዩትና በሰ ፳
ሙት ሁሉ ፡ እግዚአብሔርን እያመሰገኑ ተመለሱ ።
መዝ ፻፵፯ ፡ ፩ ።

## ክፍል ፫ ፤ በእንተ ፈጺሞቱ ሕገ ኦሪት ።

፳፩ ወአመ ተፈጸመ ሰሙን ዕለት ወሰድዎ ለሕፃን ከመ
ይግዝርዎ ወሰመይዎ ስሞ ኢየሱስ በከመ ሰመዮ
መልአክ እምቅድመ ትፅንስ ።
፳፪ ወአመ ተፈጸመ መዋዕለ ንጽሕ በከመ ሕገ ሙሴ ፤
ወሰድዎ ኢየሩሳሌም ያቅምዎ ቅድመ እግዚአ
ብሔር ።
፳፫ በከመ ጽሑፍ ውስተ ሕገ እግዚአብሔር ኵሉ ተባ
ዕት ዘይፈትሕ ማኅፀነ እሙ ቅዱሰ ይሰመይ ለእ
ግዚአብሔር ።
፳፬ ወከመ ያብኡ መሥዋዕተ በእንቲአሁ በከመ ተብህለ
ውስተ ሕገ እግዚአብሔር ዘውገ ማዕነቅ ወእመአኮሰ
ክልኤቲ እጕለ ርግብ ።

## ክፍል ፬ ፤ በእንተ ስምዖን ።

፳፭ ወሀሎ አሐዱ ብእሲ በኢየሩሳሌም ዘስሙ ስምዖን ፤
ወውእቱ ጻድቅ ወየዋህ ወይሴፎ ይርአይ መድኃኒ
ቶሙ ወፍሥሐሆሙ ለእስራኤል ወመንፈስ ቅዱስ
ላዕሌሁ ።
፳፮ ወአርአዮ መንፈስ ቅዱስ ከመ ኢይመውት ዘእንበለ
ይርአይ መሲሐ ለእግዚአብሔር ።
፳፯ ወወሰዶ መንፈስ ምኵራብ ፤ ወሶበ አብእዎ አዝማ
ዲሁ ለሕፃን ኢየሱስ ከመ ይግበሩ ሎቱ ዘበሕጉ ።
፳፰ ተወክፎ ውእቱኒ ወአንበሮ ውስተ ሕፅኑ ወባረከ
ለእግዚአብሔር ።
፳፱ ወይቤ ይእዜ ትስዕሮ ለገብርከ በሰላም ፤ እግዚእ
በከመ አዘዝከ ።
፴ እስመ ርእያ አዕይንትየ አድኅኖተከ ።
፴፩ ዘአስተዳሎከ ቅድመ ኵሉ ሕዝብከ ።
፴፪ ከመ ትክሥት ብርሃነ ለአሕዛብ ፤ ወክብረ ለሕዝብከ
እስራኤል ።
፴፫ ወዮሴፍሰ ወእሙ ያነክሩ በእንተ ዘይነብብ ላዕሌሁ ።
፴፬ ወባረከሙ ስምዖን ወይቤላ ለእሙ ማርያም ፤ ናሁ
ዝንቱ ሕፃን ሥዩም ለድቀቶሙ ወለተንሥአቶሙ
ለብዙኃን እምውስተ እስራኤል ፤ ወለትእምርት በዘ
ይትዋቀሱ ።
፴፭ ወለኪሰ ይበውእ ውስተ ልብኪ ኲናተ ኑፋቄ ከመ
ይክሥት ሕሊና ልበሙ ለብዙኃን ።

## ክፍል ፭ ፤ በእንተ ሐና ነቢይት ።

፴፮ ወሀለወት ሐና ነቢዪት ወለተ ፋኑኤል እንተ እምነ
ገደ አሴር ወኃለፈ መዋዕሊሃ ወምስለ ምታሰ ነበረት
ሰብዐተ ክረምተ እምድኅረ ነበረት በድንግልና ።

## ክፍል ፫ ፤ የኦሪትን ሕግ ስለ መፈጸሙ ።

ስምንት ቀን በተፈጸመ ጊዜም ፤ ሕፃኑን ሊገዝሩት ፳፩
ወሰዱት ፤ ሳትፀንሰው መልአኩ እንዳወጣለት ስሙ
ን ኢየሱስ አሉት ። ምዕ ፩ ፤ ፴፩ - ፶፬ ።
የመንጻትም ወራት በተፈጸመ ጊዜ ፤ እንደ ሙሴ ፳፪
ሕግ በእግዚአብሔር ፊት ያቆሙት ዘንድ ወደ ኢየ
ሩሳሌም ወሰዱት ። ዘሌዋ ፲፪ ፤ ፪ ።
"በኵር ሆኖ የሚወለድ ወንድ ልጅ ሁሉ ለእግዚአ ፳፫
ብሔር የተቀደሰ ይባል" ተብሎ በእግዚአብሔር ሕግ
እንደ ተጻፈ ። ዘፀ ፲፫ ፤ ፪ ።
በእግዚአብሔር ሕግ እንደ ታዘዘ የዋኖስ ወገን ፤ ፳፬
ወይም ሁለት የርግብ ገላግሌት ስለ እርሱ መሥዋ
ዕት አድርገው ያቀርቡለት ዘንድ ። ዘሌ ፲፪ ፤ ፫ ።

## ክፍል ፬ ፤ ስለ ስምዖን ።

በኢየሩሳሌም ስሙ ስምዖን የሚባል አንድ ሰው ፳፭
ነበር ፤ እሱ ጻድቅ ደግ ሰው ነበር ፤ የእስራኤልን ደስ
ታቸውንና ድኅነታቸውን ሊያይ ተስፋ ያደርግ ነበር ፤
መንፈስ ቅዱስም ያደረበት ነበር ። ሐጌ ፪ ፤ ፫ ።
የእግዚአብሔር መሲሕ ክርስቶስን ሳያይ እንደማይ ፳፮
ሞት መንፈስ ቅዱስ ገልጦለት ነበር ። መዝ ፹፱ ፤ ፵፱ ።
መንፈስ ቅዱስም ወደ ምኩራብ ወሰደው ፤ በሕግ ፳፯
የተጻፈውን ያደርጉለት ፤ ሕፃኑን ኢየሱስ ወደ ቤተ
መቅደስ ዘመዶቹ በአገቡት ጊዜ ። ቀኍ ፳፪ - ፳፬ ።
እርሱም ተቀብሎ በክንዱም ታቅፎ እግዚአብሔርን ፳፰
አመሰገነው ።
አቤቱ! እንደ አዘዝከ ዛሬ ባርያህን በሰላም ታሰናብ ፳፱
ተዋለህ ። ዘፍ ፵፮ ፴ ። ራእ ዮሐ ፲፬ ፤ ፲፫ ።
ዐይኖቼ ትድግናህን አይተዋልና ። ዘፍ ፵፱ ፤ ፲ - ፲፰ ። ፴
በወገንህ ፊት ሁሉ ያዘጋጀኸውን ። ኢሳ ፶፪ ፤ ፲ ። ፴፩
ለአሕዛብ ብርሃንን ፤ ለወገንህ ለእስራኤል ክብርን ፤ ፴፪
ትገልጥ ዘንድ ። ኢሳ ፵፪ ፤ ፯ ። ፵፱ ፤ ፮ ።
ዮሴፍና እናቱ ግን በእሱ ስለሚናገረው ያደንቁ ነበር። ፴፫
ስምዖንም ባረካቸው ፤ እናቱ ማርያምንም እንዲህ ፴፬
አላት ፤ ይህ ልጅ ከእስራኤል መካከል ለብዙዎች
ለመነሣታቸው በሚፈርድባቸውም ገንዘብ ለምልክት
የተዘጋጀ ነው ። ኢሳ ፰ ፤ ፲፬ ። ማቴ ፳፩ ፤ ፵፪ ።
ሮሜ ፱ ፤ ፴፪ - ፴፫ ።
ባንቺ ግን በልብሽ የሚከፋፍል ፍላፃ ይገባል ፤ የብ ፴፭
ዙዎቹን ሐሳብ ይገልጥ ዘንድ ። ዮሐ ፲፱ ፤ ፳፭ - ፳፮ ።

## ክፍል ፭ ፤ ስለ ነቢዩቱ ሐና ።

ከአሴር ወገን የምትሆን የፋኑኤል ልጅ ነቢዩቱ ሐና ፴፮
ነበረች ፤ አርጅታ ነበር ፤ በድንግልና ከኖረች በኋላ
ከባሏ ጋር ሰባት ዓመት ኖረች ።

፲፯ ዘመሥኤ ውስተ እዴሁ ወያነጽሕ ዐውደ እክሉ ወያ
ስተጋብእ ሥርናዮ ውስተ መዛግብቲሁ ፡ ወኀሠርሰ
ያውዒ በእሳት ዘኢይጠፍእ ።
፲፰ ወበ ባዕድኒ ብዙኅ ዘመሀሮሙ ለሕዝብ ወገሠፆሙ ።

ክፍል ፲ወ፫ ፡ በእንተ ተሞቅሖቱ ለዮሐንስ መጥምቅ ።

፲፱ ወከነ ዮሐንስ ይጌሥፆ ወይዘልፎ በእንተ ሄሮድያዳ
ብእሲተ ፊልጶስ እኁሁ ፡ ወበእንተ ኵሉ እኩይ ዘገ
ብረ ሄሮድስ ።
፳ ወዓዲ ወሰከ እንበይነ ዝኒ ተቀየሞ ለዮሐንስ ወዐ
ጾዎ ውስተ ቤተ ሞቅሕ ።

ክፍል ፲ወ፬ ፡ በእንተ ጥምቀቱ ለእግዚእነ ።

፳፩ ወእምድኅረ ተጠምቀ ኵሉ ሕዝብ ተጠምቀ እግዚእ
ኢየሱስኒ ፡ ወእንዘ ይጼሊ ተርኅወ ሰማይ ።

፳፪ ወወረደ መንፈስ ቅዱስ ላዕሌሁ በአምሳለ ሥጋ ርእ
የተ ርግብ ፀዓዳ ፡ ወመጽአ ቃል እምሰማይ ዘይብል
አንተ ውእቱ ወልድየ ዘአፈቅር ወኪያከ ሠመርኩ ።

ክፍል ፲ወ፭ ፡ በእንተ መጽሐፈ ትውልድ ዘኢየሱስ ።

፳፫ ወየአክል ሠላሳ ክረምቱ ለእግዚእ ኢየሱስ ፡ ወይመ
ስሎሙ ወልደ ዮሴፍ ውእቱ ።
፳፬ ወልደ ኤሊ ፡ ወልደ ማቲ ፡ ወልደ ሌዊ ፡ ወልደ
ሚልኪ ፡ ወልደ ዮና ፡ ወልደ ዮሴፍ ።
፳፭ ወልደ ማታትዩ ፡ ወልደ አሞጽ ፡ ወልደ ናሆም ፡
ወልደ ኤሰሌም ፡ ወልደ ናጌ ።
፳፮ ወልደ ማአት ፡ ወልደ ማታትዩ ፡ ወልደ ሴሜይ ፡
ወልደ ዮሴፍ ፡ ወልደ ዮዳ ።
፳፯ ወልደ ዮናን ፡ ወልደ ሬስ ፡ ወልደ ዘሩባቤል ፡ ወልደ
ሰላትያል ፡ ወልደ ኔሪ ።
፳፰ ወልደ ሚልኪ ፡ ወልደ ሐዲ ፡ ወልደ ዮሳ ፡ ወልደ
ቆሳም ፡ ወልደ ኤልሞዳም ፡ ወልደ ኤር ።
፳፱ ወልደ ዮሴዕ ፡ ወልደ አልአዛር ፡ ወልደ ዮራም ፡
ወልደ ማጣት ፡ ወልደ ሌዊ ።
፴ ወልደ ስምዖን ፡ ወልደ ይሁዳ ፡ ወልደ ዮሴፍ ፡ ወልደ
ዮናን ፡ ወልደ ኤልያቄም ።
፴፩ ወልደ ሜልያ ፡ ወልደ ማይናን ፡ ወልደ ማጣት ፡
ወልደ ናታን ፡ ወልደ ዳዊት ።
፴፪ ወልደ ዕሤይ ፡ ወልደ ኢዮቤድ ፡ ወልደ ቡዔዝ ፡
ወልደ ሰልሞን ፡ ወልደ ነአሰን ።
፴፫ ወልደ አሚናዳብ ፡ ወልደ አራም ፡ ወልደ አርኒ ፡
ወልደ ኤስሮም ፡ ወልደ ፋሬስ ፡ ወልደ ይሁዳ ።

መንሹ በእጁ ያለ ፡ ያውድማውን እህል ያጠራል ፡ ፲፯
ሥንዴውንም በጐተራዎቹ ያከማቻል ፡ ገለባውን ግን
በማይጠፋ እሳት ያቃጥለዋል ።
ለሕዝቡም ያስተማራቸው የመከራቸው ብዙ ነገር ፲፰
አለ ።

ክፍል ፲፫ ፡ ስለ ዮሐንስ መጥምቅ መታሠር ።

ዮሐንስም ፡ ሄሮድስን የወንድሙን የፊልጶስን ሚስት ፲፱
ሄሮድያዳን በማግባቱ ፡ ሄሮድስን በሚያደርገው ክፉ
ነገር ሁሉ ይገሥፀው ነበር ። ማር ፮ ፡ ፲፯ - ፲፰ ።
ደግሞም በተግሣፅ ላይ ተግሣፅ ጨመረ ፡ ስለዚህም ፳
ዮሐንስን ተቀየመውና ፡ በእስር ቤት አግብቶ ዘጋ
በት ።

ክፍል ፲፬ ፡ ጌታችን ስለ መጠመቁ ።

ሕዝቡም ሁሉ ከተጠመቁ በኋላ ፡ ጌታ ኢየሱስም ተጠ ፳፩
መቀ ፡ ሲጸልይም ሰማይ ተከፈተ ። ማቴ ፫ ፡ ፲፫ - ፲፯ ።
ማር ፩ ፡ ፱ - ፲፩ ።
መንፈስ ቅዱስም የነጭ ርግብ መልክ ባለው አካል ፳፪
አምሳል በራሱ ላይ ወረደ ፡ ከሰማይም "የምወድህ
ልጄ አንተ ነህ ፡ አንተን መረጥኩ" የሚል ቃል
መጣ ። ምዕ ፱ ፡ ፴፭ ። ፪ ጴጥ ፩ ፡ ፲፯ ።

ክፍል ፲፭ ፡ ስለ ኢየሱስ ትውልድ መጽሐፍ ።

የጌታ ኢየሱስም ዕድሜው ሠላሳ ዓመት ያህል ነበር ፡ ፳፫
የዮሴፍ ልጅም ይመስላቸው ነበር ። ምዕ ፬ ፡ ፳፪ ።
የኤሊ ልጅ ፡ የማቲ ልጅ ፡ የሌዊ ልጅ ፡ የሚልኪ ፳፬
ልጅ ፡ የዮሴፍ ልጅ ።
የማታትዩ ልጅ ፡ የአሞፅ ልጅ ፡ የናሆም ልጅ ፡ የኤ ፳፭
ሴሌም ልጅ ፡ የናጌ ልጅ ።
የማአት ልጅ ፡ የማታትዩ ልጅ ፡ የሴሜይ ልጅ ፡ የዮ ፳፮
ሴፍ ልጅ ፡ የዮዳ ልጅ ።
የዮናን ልጅ ፡ የሬስ ልጅ ፡ የዘሩባቤል ልጅ ፡ የሰላት ፳፯
ያል ልጅ ፡ የኔሪ ልጅ ።
የሚልኪ ልጅ ፡ የሐዲ ልጅ ፡ የዮሳ ልጅ ፡ የቆሳም ፳፰
ልጅ ፡ የኤልሞዳም ልጅ ፡ የኤር ልጅ ።
የዮሴዕ ልጅ ፡ የአልአዛር ልጅ ፡ የዮራም ልጅ ፡ የማ ፳፱
ጣት ልጅ ፡ የሌዊ ልጅ ።
የስምዖን ልጅ ፡ የይሁዳ ልጅ ፡ የዮሴፍ ልጅ ፡ የዮናን ፴
ልጅ ፡ የኤልያቄም ልጅ ።
የሚልያ ልጅ ፡ የማይናን ልጅ ፡ የማጣት ልጅ ፡ የና ፴፩
ታን ልጅ ፡ የዳዊት ልጅ ። ፪ ሳሙ ፭ ፡ ፲፬ ።
የዕሤይ ልጅ ፡ የኢዮቤድ ልጅ ፡ የቡዔዝ ልጅ ፡ የሰ ፴፪
ልሞን ልጅ ፡ የነአሰን ልጅ ። ሩት ፬ ፡ ፳፪ ።
የአሚናዳብ ልጅ ፡ የአራም ልጅ ፡ የአርኒ ልጅ ፡ የኤስ ፴፫
ሮም ልጅ ፡ የፋሬስ ልጅ ፡ የይሁዳ ልጅ ። ዘፍ ፳፱ ፡ ፴፭ ።

፴፬ ወልደ ያዕቆብ ፡ ወልደ ይስሐቅ ፡ ወልደ አብርሃም ፡
ወልደ ታራ ፡ ወልደ ናኮር ።
፴፭ ወልደ ሴሩግ ፡ ወልደ ራግው ፡ ወልደ ፋሌቅ ፡ ወልደ
ኤቦር ፡ ወልደ ሳላ ።
፴፮ ወልደ ቃይንም ፡ ወልደ አርፋክስድ ፡ ወልደ ሴም ፡
ወልደ ኖኅ ፡ ወልደ ላሜህ ።
፴፯ ወልደ ማቱሳላ ፡ ወልደ ሄኖክ ፡ ወልደ ያሬድ ፡ ወልደ
መላልኤል ፡ ወልደ ቃይናን ።
፴፰ ወልደ ሄኖስ ፡ ወልደ ሴት ፡ ወልደ አዳም ፡ ወልደ
እግዚአብሔር ።

### ምዕራፍ ፬ ፤

### ክፍል ፲ወ፮ ፡ በእንተ ተመክሮቱ እምዲያብሎስ ።

፩ ወመልአ መንፈስ ቅዱስ ላዕለ እግዚእ ኢየሱስ ወተ
መይጠ እምዮርዳኖስ ፡ ወወሰዶ መንፈስ ገዳመ ።

፪ ወጾመ አርብዓ መዓልተ ወአርብዓ ሌሊተ ወያሜክሮ
ሰይጣን ወኢበልዐ ወኢሰትየ ምንተኒ በውእቶን
መዋዕል ፡ ወተፈጸሞን እማንቱ መዋዕል ርኅበ ።

፫ ወይቤሎ ሰይጣን እመሰ ወልደ እግዚአብሔር አንተ
በል ዝንቱ እብን ይኩን ኅብስተ ።
፬ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ ጽሑፍ ዘይ
ብል ፡ አኮ በኅብስት ክመ ዘየሐዩ ሰብእ ፡ አላ በኵሉ
ቃል ዘይወፅእ እምአፉሁ ለእግዚአብሔር ።
፭ ወአዕረጎ ሰይጣን ውስተ ደብር ነዋኅ ወአርአዮ መን
ግሥታተ ኵሉ ዓለም ከመ ወኢ.ምንትኒ ።
፮ ወይቤሎ ሰይጣን ዘንተ ኵሎ ምኵናነ ወዘንተኒ
ክብረ ለከ እሁበከ ፡ እስመ ሊተ ተውህበ ወለዘፈቀ
ድኩ እሁብ ።
፯ ወእምከመ ሰገድከ ሊተ አንተ ቅድሜየ ለከ ይኩ
ንክ ኵሉ ።
፰ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ሑር እምድኅሬየ ሰይጣን፡
ጽሑፍ ለእግዚአብሔር አምላክከ ትስግድ ወኪያሁ
ባሕቲቶ ታምልክ ።
፱ ወወሰዶ ኢየሩሳሌም ወአቀሞ ዲበ ርእሰ ማዕዘንተ
ቤተ መቅደስ ፡ ወይቤሎ እመሰ ወልደ እግዚአብሔር
አንተ ረድ ለሊከ እምዝየ ወተወረው ።

፲ እስመ ጽሑፍ ከመ ለመላእክቲሁ ይኤዝዞሙ በእን
ቲአከ ከመ ይዕቀቡከ በኵሉ ፍናዊከ ።
፲፩ ወበእደዊሆሙ ያነሥኡከ ከመ ኢትትዐቀፍ በእብን
እግረከ ።
፲፪ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ ፡ ተብህለ ኢታ
መክሮ ለእግዚአብሔር አምላክከ ።
፲፫ ወፈጺሞ ሰይጣን አመክሮቶ በኵሉ ኀደጎ እስከ
ጊዜሁ ።



የያዕቆብ ልጅ ፡ የይስሐቅ ልጅ ፡ የአብርሃም ልጅ ፡ ፴፬
የታራ ልጅ ፡ የናኮር ልጅ ። ዘፍ ፳፩ ፡ ፪-፫ ።
የሴሩግ ልጅ ፡ የራግው ልጅ ፡ የፋሌቅ ልጅ ፡ የኤቦር ፴፭
ልጅ ፡ የሳላ ልጅ ።
የቃይናም (የቃይናን) ልጅ ፡ የአርፋክስድ ልጅ ፡ የሴም ፴፮
ልጅ ፡ የኖኅ ልጅ ፡ የላሜህ ልጅ ። ዘፍ ፭ ፡ ፫-፴፪ ።
የማቱሳላ ልጅ ፡ የሄኖክ ልጅ ፡ የያሬድ ልጅ ፡ የመላ ፴፯
ልኤል ልጅ ፡ የቃይናን ልጅ ።
የሄኖስ ልጅ ፡ የሴት ልጅ ፡ የአዳም ልጅ ፡ የእግዚአ ፴፰
ብሔር ልጅ ። ዘፍ ፭ ፡ ፩-፫ ።

### ምዕራፍ ፬ ፤

### ክፍል ፲፮ ፡ ከዲያብሎስ ስለ መፈተኑ ።

መንፈስ ቅዱስም በጌታ በኢየሱስ ላይ መላ ፡ ከዮርዳ ፩
ኖስም ተመለሰ ፡ መንፈስም ወደ ምድረ በዳ ወሰ
ደው ። ማቴ ፬ ፡ ፩-፲፩ ። ማር ፩ ፡ ፲፪-፲፫ ።
አርባ መዓልት አርባ ሌሊት ጾመ ፡ ሰይጣንም ይፈት ፪
ነው ነበር ፡ በነዚያ ቀኖች ምንም ምን አልበላም
አልጠጣም ፡ እነዚያ ቀኖች ከተፈጸሙ በኋላ ተራበ ።
ዘፀ ፴፬ ፡ ፳፰ ።
ሰይጣንም አንተ የእግዚአብሔር ልጅ ከሆንክ ይህ ፫
ደንጊያ እንጀራ ይሁን በል አለው ።
ጌታ ኢየሱስም መልሶ ፡ "ሰው የሚድን ከእግዚአብ ፬
ሔር አፍ በሚወጣው ቃል ነው እንጂ ፡ በእንጀራ
ብቻ አይደለም የሚል ተጽፏል" አለው ። ዘዳ ፰ ፡ ፫ ።
ሰይጣንም ወደ ረጅም ተራራ አውጥቶ የዓለምን ፭
መንግሥታት ሁሉ በቅጽበት አሳየው ።
ሰይጣን እንዲህ አለው ፡ ይህን ሁሉ ግዛት ፡ ይህን ፮
ንም ክብር ላንተ እሰጥሃለሁ ፡ ለእኔ ተሰጥቷልና ፡
ለወደድኩትም እሰጠዋለሁና ።
አንተ በፊቴ ብትሰግድልኝ ሁሉ ላንተ ይሁንልህ ። ፯

ጌታ ኢየሱስ መልሶ "ሰይጣን ከኋላዬ ሂድ ፡ ለእግዚ ፰
አብሔር ለአምላክህ ልትሰግድ ፡ እሱንም ብቻ ልታ
መልክ" ተጽፏልና አለው ፡ ዘዳ ፲ ፡ ፲፪ ።
ወደ ኢየሩሳሌም ወስዶ በቤተ መቅደሱ የመዓዝን ፱
ጫፍ ላይ አቆመውና ፡ እንዲህ አለው ፡ የእግዚአብ
ሔር ልጅ ከሆንክስ አንተ ራስህ ከዚህ በታች ወር
ብለህ ውረድ ።
"በመንገድህ ይጠብቁህ ዘንድ መላእክትን እንደሚያ ፲
ዛቸው ተጽፏልና" ። መዝ ፺፩ ፡ ፲፩-፲፪ ።
"እግርህንም እንዳትሰነክል በእጃቸው ያነሡሃል" ። ፲፩

ጌታ ኢየሱስም መልሶ "ፈጣሪህ እግዚአብሔርን ፲፪
አትፈታተነው ተብሏል" አለው ። ዘዳ ፮ ፡ ፲፮ ።
ሰይጣንም በዚህ ሁሉ እሱን መፈታተኑን ከፈጸመ ፲፫
በኋላ እስከ ጊዜው ተወው ። ዮሐ ፲፬ ፡ ፴ ። ዕብ
፬ ፡ ፲፭ ።

፴፯ ወከነት መዓስብተ ሰማንያ ወአርባዕተ ክረምተ ፡ ወኢ
ትወጽእ እምቤተ መቅደስ መዓልተ ወሌሊተ እንዘ ትትቀ
ነይ በጾም ወበጸሎት ፡፡
፴፰ ወተንሥአት ሶቤሃ ወገነየት ወአእኰተቶ ለእግዚአ
ብሔር ወነገረት በእንቲአሁ ለኵሎሙ እለ ይሴፈዉ
መድኃኒታ ለኢየሩሳሌም ፡፡
፴፱ ወፈጺሞሙ ኵሎ ዘበሕገ እግዚአብሔር አተዉ
ገሊላ ሀገሮሙ ፡፡
፵ ወልህቀ ሕፃን ወጸንዐ በመንፈስ ቅዱስ ፡ ወምሉእ
ጥበበ ወፍጹም በጸጋ እግዚአብሔር ዘላዕሌሁ ፡፡

ክፍል ፲ወ፩ ፡ በእንተ ተረክቦቱ ማእከለ ሊቃውንት ፡፡

፵፩ ወየሐውሩ አዝማዲሁ ኢየሩሳሌም ለለዓመት ለበ
ዓለ ፋሲካ ፡፡
፵፪ ወአመ ኮነ ፍጹመ ሎቱ ዐሠርቱ ወክልኤቱ ክረ
ምት ዐርጉ ለበዓል ኢየሩሳሌም በከመ ያለምዱ ፡፡
፵፫ ወሰሊጦሙ ግብሮሙ አተዉ ገሊላ ሀገሮሙ ፡ ወሕ
ፃንሰ ኢየሱስ ነበረ ኢየሩሳሌም ወኢያእመሩ ዮሴፍ
ወእሙ ፡፡
፵፬ ወይመስሎሙ ከመ ዘበፍኖት ሀሎ ምስለ ሰብእ ፡
ወበጺሖሙ ኅሠሥዎ በዕለታ ኀበ አዝማዲሁ ወኀበ
እለ የአምርዎ ፡ ወኢረከብዎ ፡፡
፵፭ ወሰበ ኢረከብዎ ተሠውጡ ኢየሩሳሌም እንዘ የኃ
ሥሥዎ ፡፡
፵፮ ወእምዝ በሣልስታ ረከብዎ በምኵራብ እንዘ ይነብር
በማእከለ ሊቃውንት ወያጸምኦሙ ወይሴአሎሙ ፡፡
፵፯ ወያነክርዎ ኵሎሙ እለ ሰምዑ ጥበበ ወአውሥኦቶ ፡፡
፵፰ ወሰበ ርእይዎ ደንገፁ ፡ ወትቤሎ እሙ ወልድየ ለም
ንት ከመዝ ረሰይከነ እስመ ናሁ አቡከ ወአነኒ ሠራ
ሕነ እንዘ ነኀሥሠከ ፡፡
፵፱ ወይቤሎሙ ለምንት ተኃሥሡኒ ፡ ኢያአመርክሙኑ
ከመ ይደልወኒ አሀሉ ውስተ ዘአቡየ ቤት ፡፡
፶ ወእሙንቱሰ ኢለበዉ ቃሎ ዘይቤሎሙ ፡፡
፶፩ ወሖረ ወወረደ ምስሌሆሙ ናዝሬተ ፡ ወኮነ ይትኤ
ዘዝ ሎሙ ወእሙሰ ተዐቅብ ዘንተ ኵሎ ነገረ ወት
ወድዮ ውስተ ልባ ፡፡
፶፪ ወእግዚእ ኢየሱስ ልህቀ ወዐብየ በጥበብ ወበምክር
ወበጸጋ ፡ በኀበ እግዚአብሔር ወበኀበ ሰብእ ፡፡

ምዕራፍ ፫ ፤

ክፍል ፲ወ፪ ፡ በእንተ ስብከተ ዮሐንስ መጥምቅ ፡፡

፩ ወአመ ዐሠርቱ ወኃምስቱ ዐመተ መንግሥቱ ለጢ
ባርዮስ ቄሣር እንዘ ጲላጦስ ጸንጤናዊ መልአከ
ይሁዳ ፡ ወሄሮድስ ንጉሥ ላዕለ ገሊላ ፡ ወፊልጶስ



ሰማንያ አራት ዓመት ግን ፈት ሆና ኖረች ፡ በጾምና ፴፯
በጸሎትም እያገለገለች ቀንም ሌትም ከምኵራብ አት
ወጣም ነበር ፡፡ ፩ ጢሞ ፭ ፡ ፭ ፡፡
ያን ጊዜም ተነሥታ አመነች ፡ እግዚአብሔርንም አመ ፴፰
ሰገነችው ፡ የኢየሩሳሌም ድኅነት ተስፋ ለሚያደርጉ
ሁሉ የእርሱን ነገር ነገረች ፡፡ ቊ ፳፭ ፡፡
በእግዚአብሔር ሕግ የተጻፈውን ከፈጸሙ በኋላ ፴፱
ወደ ገሊላ ወደ አገራቸው ተመለሱ ፡፡ ቊ ፳፪ ፡፡
ሕፃኑም አደገ በዕውቀትም ጸና ጥበብንም የተመላ ፵
ነበር ፡ ባለውም በእግዚአብሔር ጸጋ ፍጹም ነበር ፡፡
ቊ ፶፪ ፡፡ ምዕ ፩ ፡ ፹ ፡፡

ክፍል ፲፩ ፡ በሊቃውንት መካከል ስለ መገኘቱ ፡፡

ዘመዶቹም በየመቱ በፋሲካ በዓል ወደ ኢየሩሳሌም ፵፩
ይሄዱ ነበር ፡፡ ዘፀ ፳፫ ፡ ፲፬ - ፲፯ ፡፡
ዐሥራ ሁለት ዓመትም በሆነው ጊዜ እንደ አስለ ፵፪
መዱ ለበዓል ወደ ኢየሩሳሌም ወጡ ፡፡
ሥራቸውንም ጨርሰው ወደ አገራቸው ወደ ገሊላ ፵፫
ገቡ ፡ ሕፃኑ ኢየሱስ ግን በኢየሩሳሌም ቀረ ፡ ዮሴፍና
እናቱ አላወቁም ነበር ፡፡
በመንገድም ከሰዎች ጋር ያለ መስሏቸው ነበር ፡ ፵፬
ከደረሱም በኋላ ዕለቱን ከዘመዶቹ ከሚያውቁት
ዘንድ ፈለጉት ፡ አላገኙትም ፡፡
ባላገኙትም ጊዜ እየፈለጉት ወደ ኢየሩሳሌም ተመ ፵፭
ለሱ ፡፡
ከዚህ በኋላ በሦስተኛው ቀን በምኵራብ ፡ በሊቃው ፵፮
ንት መካከል ተቀምጦ ሲሰማቸውና ሲጠይቃቸው
አገኙት ፡፡
የሰሙት ሁሉ አስተዋይነቱን አመላለሱን ያደንቁ ፵፯
ነበር ፡፡ ምዕ ፬ ፡ ፳፪ ፡፡ ዮሐ ፯ ፡ ፲፭ ፡፡
ባዩትም ጊዜ ደነገጡ ፡ እናቱም ልጄ! ለምን እንዲህ ፵፰
አደረግኸን ፡ እነሆ እኔም አባትህም ስንፈልግህ ብዙ
ደከምን አለችው ፡፡
እርሱም ለምን ትፈልጉኛላችሁ? በአባቴ ቤት ልኖር ፵፱
እንደሚገባኝ አላወቃችሁምን? አላቸው ፡፡ ዮሐ ፪ ፡ ፲፯ ፡፡
እነሱ ግን የነገራቸውን ቃሉን አላስተዋሉም ፡፡ ፶
ከነርሱም ጋር ወደ ናዝሬት ወርዶ ሄደ ፡ ይታዘዝላ ፶፩
ቸውም ነበር ፡ እናቱ ግን ይህን ሁሉ ነገር ታስተ
ውል ፡ በልቧም ታኖረው ነበር ፡፡ ቊ ፲፱ ፡፡ ዘፀ ፳ ፡ ፲፪ ፡፡
ጌታ ኢየሱስ በእግዚአብሔር ዘንድ በሰውም ዘንድ ፶፪
በጸጋ ፡ በምክር ፡ በጥበብ አደገ ፡ ጕለመሰ ፡፡ ቊ ፵ ፡፡
ዕብ ፪ ፡ ፯ ፡፡

ምዕራፍ ፫ ፤

ክፍል ፲፪ ፡ ስለ መጥምቁ ስለ ዮሐንስ ስብከት ፡፡

ጢባርዮስ ቄሣር በነገሠ በዐሥራ አምስት ዓመት ፡ ፩
ጰንጤናዊው ጲላጦስ የይሁዳ ገዥ ሆኖ ሳለ ፡ ሄሮድ
ስም በገሊላ ላይ ንጉሥ ፡ ወንድሙ ፊልጶስም የኢ

እኁሁ መልአከ ኢጡርያስ ወለብሔረ ጥራኮኒዶስ ፣
ወሊሳንዩስ ሀቢ እንተ ሳብላኔስ ።
፪ ወአመ ሐና ወቀያፋ ሊቃነ ክህናት ፡ መጽአ ቃለ እግ
ዚአብሔር ላዕለ ዮሐንስ ወልደ ዘካርያስ በገዳም ።

፫ ወዖደ አድያመ ዮርዳኖስ ወሰበከ ጥምቀተ ለንስሐ
በዘይትኀደግ ኀጢአት ።

፬ በከመ ይብል ቃለ መጽሐፈ ኢሳይያስ ነቢይ ዘይቤ ፣
ናሁ ቃለ ዓዋዲ ዘይሰብክ በገዳም ወይብል ጺሑ
ፍኖተ እግዚአብሔር ወዐርዩ መጽያሕቶ ።

፭ ኵሉ ማዕምቅ ይምላእ ፡ ወኵሉ ደብር ወወግር
ይትሐት ፡ ወይኩን መብእስ መጽያሕተ ርቱዐ ፣ ወይ
ዕሬ ፍኖት መብእስ ።
፮ ወይርአይ ኵሉ ዘነፍስ አድኅኖቶ ለእግዚአብሔር ።

፯ ወይቤሎሙ ዮሐንስ ለሕዝብ እለ መጽኡ ኀቤሁ ያጥ
ምቆሙ ፡ ትውልደ ሰበድዐት መኑ ነገረክሙ ታም
ስጡ እመቅሠፍት ዘይመጽእ ።

፰ ግበሩ እንከ ፍሬ ዘይደልወክሙ ለንስሐ ፡ ወኢይም
ሰልክሙ በብሂለ ዘትብሉ ሀሎ አቡነ አብርሃም ፡
እብለክሙ ከመ ይክል እግዚአብሔር አንሥአ
ውሉደ ፡ ለአብርሃም እምእላንቱ አእባን ።

፱ እስመ ናሁ ወድአ ተሰይመ ጕድብ ኀበ ጕንደ
ዕፀው ፣ ወለኵሉ ዕፅ ዘኢይፈሪ ፍሬ ሠናየ ይገዝ
ምዎ ወውስተ እሳት ይወድይዎ ።
፲ ወተስእልዎ ሕዝብ ወይቤልዎ ምንተ ንግበር ።

፲፩ ወአውሥአ ወይቤሎሙ ዘቦ ክልኤ ልብስ ክዳናተ
የሀብ ለዘአልቦ ፡ ወዘሂቦ እክል ከማሁ ይግበር ።

፲፪ ወመጽኡ መጸብሐንሂ ያጥምቆሙ ፣ ወተስእልዎ
ወይቤልዎ ሊቅ ምንተ ንግበር ።
፲፫ ወይቤሎሙ አልቦ ዘትገብሩ ፈድፋደ እምዘተአዘዝ
ክሙ ።
፲፬ ወተስእልዎ ሐራሂ ወይቤልዎ ፡ ንሕነኬ ምንተ ንግ
በር ፣ ወይቤሎሙ ኢትሂዱ ፣ ወኢትትዓገሉ መነሂ ፣
አላ ንበሩ በበሲሳይክሙ ።
፲፭ ወሐለዩ ኵሉ ሕዝብ በልቦሙ ወመሰሎሙ ዮሐንስ
ከመ ውእቱ ክርስቶስ ።
፲፮ ወአውሥአ ዮሐንስ ወይቤሎሙ ለኵሎሙ አንሰ
አጠምቀክሙ በማይ ፡ ወይመጽእ ዘይጸንዐኒ እፍታሕ
ቶታነ አሣእኒሁ እምእገሪሁ ፣ ወውእቱ ያጠምቀክሙ
በመንፈስ ቅዱስ ወበእሳት ።

ጡርያስና የጥራኮኒዶስ ገዥ ፣ ሊሳንዩስም የሳብላኔስ
ገዥ ሆነው ሳሉ ።
ሐና እና ቀያፋም የክህናት አለቆች በነበሩበት ፪
ወራት ፣ የእግዚአብሔር ቃል በምድረ በዳ ወደ ዘካ
ርያስ ልጅ ወደ ዮሐንስ መጣ ።
ኃጢአት በሚሠረይበት ገንዘብ ለንስሐ የሚያበቃ ፫
ጥምቀትን እየሰበከ ፣ የዮርዳኖስን አውራጃ ዞረ ።
ማቴ ፫ ፡ ፩ - ፪ ። ማር ፩ ፡ ፩ - ፰ ።
በምድረ በዳ የሚጮኽ አዋጅ ነጋሪ እነሆ ያለ የነ ፬
ቢዩ የኢሳይያስ መጽሐፍ ቃል እንደሚለው ፣ እሱም
የእግዚአብሔርን መንገድ ጥረጉ ፣ ጐዳናውንም አስ
ተካክሉ ፣ ይላል ። ኢሳ ፵ ፡ ፫ - ፬ ።
ጐድጓዳው ሁሉ ይሞላ ፣ ተራራውም ኮረብታውም ፭
ሁሉ ዝቅ ይበል ፣ ሰንከልካላውም የተካከለ ጥርጊያ
ይሁን ፣ ወጣ ገባው መንገድ ይስተካከል ።
ነፍስ ያለው ሁሉ የእግዚአብሔርን ትድግና ይይ ። ፮
ኢሳ ፶፪ ፡ ፲ ።
ዮሐንስም ሊያጠምቃቸው የመጡትን ሰዎች እን ፯
ዲህ አላቸው ፣ እናንት የእፍኝት እባብ ልጆች ከሚ
መጣው መቅሠፍት ታመልጡ ዘንድ ማን ነገራችሁ?
ማቴ ፳፫ ፡ ፴፫ ።
እንግዲህ ለንስሐ የሚያበቃችሁን ሥራ ሥሩ ፣ አብ ፰
ርሃም አባታችን አለን እንደምትሉ አይምሰላችሁ ፣
እግዚአብሔር ከእነዚህ ደንጎች ለአብርሃም ልጅን
ማስነሣት እንደሚችል እነግራችኋለሁ ። ማቴ ፫ ፡ ፩ ።
ዮሐ ፰ ፡ ፴፱ ።
አሁን ምሳር በዛፎች ላይ ተቃጥቷልና ፣ መልካም ፱
ፍሬ የማያፈራውን ዕንጨት ሁሉ ይቈርጡታል ወደ
እሳትም ይጨምሩታል ። ማቴ ፯ ፡ ፲፱ ። ዮሐ ፲፭ ፡ ፪ - ፯ ።
ሕዝቡም ምን እናድርግ? ብለው ጠየቁት ። ግብ ፲
ሐዋ ፪ ፡ ፴፯ ።
ሁለት ልብስ ያለው ለሌለው ልብስ ይስጥ ፡ እህል ፲፩
ያለውም እንዲሁ ያድርግ ። ኢሳ ፶፰ ፡ ፯ ። ያዕ ፪ ፡
፲፫ - ፲፭ ።
ቀራጮች ሊያጠምቃቸው መጡና መምህር ! ምን ፲፪
እናድርግ ? ብለው ጠየቁት ። ማቴ ፭ ፡ ፵፯ ።
ከታዘዛችሁት አትርፋችሁ የምታደርጉት አይኑር ፲፫
አላቸው ።
ጭፍሮችም መጥተው እኛስ ምን እናድርግ? አሉት ፣ ፲፬
በየገንዘባችሁ ኑሩ እንጂ ፣ ማንንም አትቀሙ ፣ አትበ
ድሉ አላቸው ። ዘሌ ፲፱ ፡ ፲፫ - ፳ ።
ሕዝቡም ሁሉ ዮሐንስ ፡ ክርስቶስ እንደሆነ በልባ ፲፭
ቸው ያስቡ ነበር ። ዮሐ ፩ ፡ ፲፱ - ፳ ።
ዮሐንስም መልሶ ሁሉንም እንዲህ አላቸው ፡ እኔ ፲፮
በውኃ አጠምቃችኋለሁ ፡ ግን የሚበልጠኝ የጫማ
ውን ጠፍር እንኳ ልፈታለት የማይገባኝ ይመጣል ፣
እርሱ በመንፈስ ቅዱስ በእሳትም ያጠምቃችኋል ።
ማቴ ፫ ፡ ፲፩ - ፲፪ ። ዮሐ ፩ ፡ ፳፮ ።

## ክፍል ፲ወ፯ ፡ በእንተ ቀዳሚ ስብከቱ ።

፲፬ ወተመይጠ እግዚእ ኢየሱስ በኃይለ መንፈስ ቅዱስ ወሖረ ገሊላ፡ ወተሰምዐ ነገሩ በኵሉ በሐውርት ።

፲፭ ወይሜህሮሙ በኵሉ ምኵራባቲሆሙ ወያነክሩ ምህሮቶ ወይሴብሕዎ ኵሉ ወያከብርዎ ።

## ክፍል ፲ወ፰ ፡ በእንተ ስብከቱ በናዝሬት ።

፲፮ ወሖረ ናዝሬት ኀበ ተሐፅነ ወቦአ ምኵራበ በዕለተ ሰንበት በከመ ያለምድ ፡ ወተንሥአ ያንብብ ።

፲፯ ወወሀብዎ መጽሐፈ ኢሳይያስ ነቢይ ፡ ወከሢቶ መጽሐፈ ረከበ መካነ ኀበ ዘይብል ።

፲፰ መንፈሰ እግዚአብሔር ላዕሌየ ዘበእንቲአሁ ቀብአኒ እዜንዎሙ ለነዳያን ፈነወኒ ፡ ወእስብክ ሎሙ ግዕዛነ ለፂዉዋን ፡ ወአስተፍሥሖሙ ለኅዙናን ፡ ወይርአዩ ዕዉራን ፡ ወአንግፎሙ ለግፉዓን ፡ ወእፍትሖሙ ለሙቁሓን ፡ ወእፈውሶሙ ለቁሱላን ።

፲፱ ወእስብክ ዐመተ እግዚአብሔር ኅሬተ ወዘኮነ መዋዕለ ።

፳ ወከደነ መጽሐፈ ወመጠዎ ለላእክ ወነበረ ፡ ወአንሥኡ አዕይንቲሆሙ ኵሎሙ እለ ሀለዉ ውስተ ምኵራብ ወነጸርዎ ።

፳፩ ወአኀዘ ይበሎሙ ፡ ዮም በጽሐ ቃለ ዝንቱ መጽሐፍ ወተሠልጠ ውስተ ዕዘኒክሙ ።

፳፪ ወእለ ሰምዕዎ ኵሎሙ አንከሩ ሞገሰ ቃሉ ወሣዕሣዐ አፉሁ ፡ ወይቤሉ አኮኑ ዝንቱ ውእቱ ወልደ ዮሴፍ ።

፳፫ ወይቤሎሙ በኑ ትብሉኒ ኵልክሙ ዛተ ምሳሌ ዐቃቤ ሥራይ ፈውስ ርእሰከ ኵሎ ዘሰማዕነ ዘገበርከ በቅፍርናሆም ግበር በዝየኒ በሀገርከ ።

፳፬ ወይቤሎሙ አማን እብለክሙ አልቦ ነቢይ ዘይከብር በሀገሩ ።

፳፭ አማን እብለክሙ ብዙኃት መበለታት ሀለዋ በውስተ እስራኤል በመዋዕለ ኤልያስ ነቢይ አመ ተዐፅወ ሰማይ ሠለስተ ዐመተ ወስድስተ አውራኀ እስከ ኮነ ረኃብ ዐቢይ ውስተ ኵሉ ምድር ።

፳፮ ወኢተፈነወ ኤልያስ ኀበ አሐቲ እምኔሆን ዘእንበለ ኀበ አሐቲ ብእሲት መበለት ዘሀለወት በሰራጽታ ዘሲዶና ።

፳፯ ወብዙኃን እለ ለምጽ ሀለዉ በውስተ እስራኤል አመ



## ክፍል ፲፯ ፡ ስለ መጀመሪያ ትምህርቱ ።

ጌታ ኢየሱስም በመንፈስ ቅዱስ ኃይል ተመልሶ ወደ ገሊላ ሄደ ፡ ወሬውም በሀገሩ ሁሉ ተሰማ ። ማቴ ፬ ፡ ፲፪ - ፲፯ ። ማር ፩ ፡ ፲፬ - ፲፭ ። ፲፬

በየምኩራባቸውም ሁሉ ያስተምራቸው ነበር ፡ ትምህርቱንም ያደንቁ ነበር ፡ ሁሉም ያመሰግኑትና ያከብሩትም ነበር ። ፲፭

## ክፍል ፲፰ ፡ በናዝሬት ስለ ማስተማሩ ።

ወደ አደገበት ወደ ናዝሬት ሄደና በሰንበት (ቅዳሜ) ቀን እንዳስለመደ ወደ ምኵራብ ገባ ፡ ሊያነብም ተነሣ ። ማቴ ፲፫ ፡ ፶፫ ። ማር ፮ ፡ ፩ - ፮ ። ፲፮

የነቢዩ የኢሳይያስን መጽሐፍ ሰጡት ፡ መጽሐፉንም በገለጠ ጊዜ እንዲህ የሚል የተጻፈበትን ሥፍራ አገኘ ። ፲፯

"የእግዚአብሔር መንፈስ በላዬ ነው ፡ ስለዚህም ቀብቶ ለድኆች የምሥራች እነግራቸው ዘንድ ላከኝ፡ ለተማረኩትም ነፃነትን እሰብክላቸው ዘንድ ፡ ያዘኑትንም ደስ አሰኛቸው ዘንድ ፡ ዕዉሮቹም ያዩ ዘንድ ፡ የተገፉትንም አድናቸው ዘንድ ፡ የታሠሩትንም እፈታቸው ዘንድ ፡ የቈሰሉትንም አድናቸው ዘንድ" ። ኢሳ ፷፩ ፡ ፩ - ፪ ። ፲፰

የተመረጠችውን የእግዚአብሔርን ዓመትና የሆነውን ቀን አስተምር ዘንድ ። ዘሌ ፳፭ ፡ ፲ ። ፲፱

መጽሐፉንም አጥፎ ለተላላኪው ሰጠውና ተቀመጠ፡ በምኵራቡም ያሉት ሁሉ ዓይናቸውን አቅንተው አተኵረው አዩት ። ፳

እሱም የዚህ የመጽሐፍ ነገር ዛሬ ደረሰ ፡ ወደ ጆሮአችሁም ገባ ይላቸው ጀመር ። ፳፩

የሰሙትም ሁሉ የአንደበቱን ቅልጥፍና የንግግሩን መከናወን አደነቁ ፡ ግን ይህ የዮሴፍ ልጅ አይደለምን ፡ አሉ ። መዝ ፸፫ ፡ ፫ ። ኢሳ ፶ ፡ ፬ ። ፳፪

እርሱም በውኑ ሁላችሁም ባለመድኃኒት ራስህን በቅፍርናሆም ያደረግኸውን የሰማነውን ሁሉ በዚህ በሀገርህ ደግሞ አድርግ ብላችሁ ይህቺን ተረት ትተርቱብኛላችሁ አላቸው ። ፳፫

እንዲህም አላቸው ፡ እውነት እነግራችኋለሁ ፡ መምህር በሀገሩ አይከብርም ። ዮሐ ፬ ፡ ፵፬ ። ፳፬

እውነት እነግራችኋለሁ ፡ በምድር ሁሉ ረኃብ እስኪሆን ድረስ ሰማይ ሦስት ዓመት ከስድስት ወር በተዘጋበት በነቢዩ በኤልያስ ዘመን ፡ በእስራኤል ውስጥ ብዙ ባልቴቶች ነበሩ ። ፩ ነገ ፲፯ ፡ ፩ - ፱ ። ፲፰ ፡ ፩ - ፲ ። ፳፭

ኤልያስ ከነዚያ ወደ አንዲቱ አልተላከም ፡ የሲዶና ዕፃ በምትሆን በሰራጵታ ወደምትኖር ወደ አንዲት ባልቴት ሴት ነው እንጂ ። ፳፮

በነቢዩ በኤልሳዕ ዘመንም በእስራኤል ውስጥ ብዙ ፳፯

መዋዕለ ኤልሳዕ ነቢይ ወኢነጽሐ አሐዱሂ እምኔ
ሆሙ ዘእንበለ ንእማን ሶርያዊ ።
፳፰ ወተምዑ ኵሎሙ እለ ሀለዉ በምኵራብ ሰሚዖሙ
ዘንተ ።
፳፱ ተንሥኡ ሰቤሃ ወአውፅእዎ አፍአ እምሀገር ወወሰ
ድዎ ውስተ ሕፅነ ርእሰ ደብር ዘተነድቀት ላዕሌሁ
ሀገሮሙ ከመ ያጽድፍዎ ።
፴ ወውእቱሰ ኀለፈ እንተ ማእከሎሙ ወሖረ ።

## ክፍል ፲ወ፱ ፡ በእንተ ኀዲጎቱ ናዝሬተ ፡ ወሐዊሮቱ ቅፍርናሆም ።

፴፩ ወወረደ ቅፍርናሆም ሀገረ ገሊላ ወመሀሮሙ በሰ
ንበት ።

፴፪ ወያነክሩ ምህሮቶ እስመ በትእዛዝ ውእቱ ቃሉ ።

## ክፍል ፳ ፡ በእንተ አሕይዎቱ ዘጋኔን ።

፴፫ ወሀሎ በምኵራብ አሐዱ ብእሲ ዘጋኔን እኩይ ላዕ
ሌሁ ወከልሐ በዓቢይ ቃል ።
፴፬ ወይቤ ምንት ብየ ምስሌከ ኢየሱስ ናዝራዊ መጻእ
ከኑ ታጥፍአነ ፡ አአምረከ መኑ አንተ ቅዱሱ ለእግ
ዚአብሔር ።
፴፭ ወገሠፆ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ ተፈጸም ወፃእ
እምኔሁ ወነፅኖ ጋኔኑ ማእከለ ምኵራብ ፡ ወወፅአ
እምኔሁ ወኢነከዮ ወኢምንተኒ ።
፴፮ ወደንገፁ ኵሎሙ ወተናገሩ በበይናቲሆሙ ወይ
ቤሉ ፡ ምንትኑ ዝ ነገር እስመ በትእዛዝ ወበኃይል
ይኤዝዞሙ ለአጋንንት እኩያን ወይወፅኡ ።

፴፯ ወወፅአ ወተሰምዓ ነገሩ በኵሉ በሐውርተ አድያም ።

## ክፍል ፳ወ፩ ፡ በእንተ ሐማተ ጴጥሮስ ወከልአን ሕሙማን ።

፴፰ ወወፂአ እምኵራብ በአ ቤተ ስምዖን ወሐማቱ ለስ
ምዖን ተሐምም ዐቢየ ፈጸንተ ወነገርዎ ወሰአልዎ
በእንቲአሃ ።

፴፱ ወቆመ ኀቤሃ ወገሠፆ ለፈፀንታ ወኃደጋ ሶቤሃ ፡ ወተ
ንሥአት ወተልእከቶሙ ።

፵ ወሶበ የዐርብ ፀሐይ አምጽኡ ኀቤሁ ኵሎ ድዉያነ
ወሕሙማነ ደዌ ዘዘዚአሁ ፡ ወለለአሐዱ እምኔሆሙ
አንበረ እዴሁ ዲቤሆሙ ወፈወሶሙ ።



ለምጻሞች ነበሩ ፡ ከሶርያዊው ከንእማን በቀር ከነ
ዚያ አንድ ስንኳን አልነፃም ። ፪ ነገ ፭ ፡ ፲፬ ።
በምኵራብ ያሉም ሁሉ ይህን ሰምተው ተቈጡ ። ፳፰
ግብ ሐዋ ፳፪ ፡ ፳፪ ።
ያን ጊዜም ተነሥተው ከከተማ ወደ ውጭ አወጡት ፡ ፳፱
ገፍተውም ይጥሉት ዘንድ አገራቸው በላይ ተሠር
ታበት ወደ አለችው ተራራ ጫፍ አጠገብ ወሰዱት ።
እርሱ ግን በመካከላቸው አልፎ ሄደ ። ዮሐ ፰ ፡ ፶፱ ። ፴

## ክፍል ፲፱ ፡ ናዝሬትን ትቶ ፡ ወደ ቅፍርናሆም ስለ መግባቱ ።

የገሊላ ዕፃ ወደምትሆን ቅፍርናሆም ወርዶ ፡ በሰን ፴፩
በት (በቅዳሜ) አስተማራቸው ። ማቴ ፬ ፡ ፲፫ - ፲፯ ።
ማር ፩ ፡ ፳፩ - ፳፰ ።
ትምህርቱንም ያደንቁ ነበር ፡ አነጋገሩ በትእዛዝ ፴፪
ነውና ። ማቴ ፯ ፡ ፳፰-፳፱ ። ኤር ፳፫ ፡ ፳፱ ። ዮሐ ፯ ፡ ፵፮ ።

## ክፍል ፳ ፡ ጋኔን የያዘውን ስለ ማዳኑ ።

በምኵራብም ክፉ ጋኔን የያዘው አንድ ሰው ነበር ፡ ፴፫
በታላቅ ቃልም ጮኸ ።
የናዝሬቱ ኢየሱስ ሆይ! ካንተ ጋር ምን አለኝ? ያለ ፴፬
ጊዜያችን ልታጠፋን መጣህን? የእግዚአብሔር
ቅዱስ ሆይ! አንተ ማን እንደሆንክ አውቄሃለሁ አለ ።
ጌታ ኢየሱስም ዝም በልና ከእሱ ውጣ ብሎ ገሠ ፴፭
ፀው ፡ ጋኔኑም በምኵራቡ መካከል ጣለውና ከእሱ
ወጣ ፡ ግን ምንም አልጐዳውም ።
ሁሉም ደንግጠው ይህ ነገር ምንድር ነው? ክፉዎች ፴፮
አጋንንትን በትእዛዝ በኃይል ያዛቸዋል ፡ እነሱም
ይታዘዙታልና ብለው እርስ በርሳቸው ተነጋገሩ ።
፩ ጴጥ ፫ ፡ ፳፪ ።
ወሬውም በአካባቢው ባሉ መንደሮች ሁሉ ወጥቶ ፴፯
ተሰማ ።

## ክፍል ፳፩ ፡ ስለ ጴጥሮስ አማትና ፡ ስለ ሌሎችም በሽተኞች ።

ከምኵራቡም ወጥቶ ወደ ስምዖን ቤት ገባ ፡ የጴጥ ፴፰
ሮስ አማትም በብርቱ የሆድ ዝማ ታማ ነበርና ፡ የእ
ርሷን ነገር ነግረው ለመኑት ። ማቴ ፰ ፡ ፲፬ - ፲፯ ።
ማር ፩ ፡ ፳፱ - ፴፱ ።
በአጠገቧም ቆሞ ሆድ ዝማዋን ገሠፀው ፡ ወዲያ ፴፱
ውም ተዋትና ተነሥታ አገለገለቻቸው ። ምዕ ፲ ፡
፵ ። ማቴ ፰ ፡ ፲፭ - ፲፯ ።
ፀሐይም በገባ ጊዜ ልዩ ልዩ ደዌ የታመሙትንና ፵
ድውያኑን ሁሉ አመጡለት ፡ ከነሱም በእያንዳንዱ
ላይ እጁን ጭኖ ፈወሳቸው ።

፵፩ ወብዙኃን አጋንንት ይወፅኡ ወይኬልሑ ወይብልዎ
አንተ ውእቱ ክርስቶስ ወልደ እግዚአብሔር፡ ወይ
ጌሥፆሙ ወኢያበውሖሙ ይንብቡ ዘንተ እስመ የአ
ምርዎ ከመ ውእቱ ክርስቶስ ።

፵፪ ወጸቢሖ ወፅአ ወሖረ ውስተ ገዳም ወኃሠሥዎ
ሕዝብ ወሖሩ ኀቤሁ ወአኀዝዎ ወአቀምዎ ከመ ኢይ
ኅልፍ እምኔሆሙ ።
፵፫ ወይቤሎሙ ለካልአትኒ አህጉር ሀለወኒ እዜንዎን
በእንተ መንግሥተ እግዚአብሔር፡ እስመ እንበይነ
ዝንቱ ተፈነውኩ ።
፵፬ ወይሰብክ በምኵራባተ ገሊላ ።

ምዕራፍ ፭፤

<u>ክፍል ፳ወ፪፡ በእንተ ተጸውዖተ ስምዖን ።</u>

፩ ወሀለወ ኀቤሁ ሰብእ ብዙኃን ወያጸምዑ ቃለ እግ
ዚአብሔር፡ ውእቱሰ ይቀውም መንገለ ሐይቀ ባሕረ
ጌንሴሬጥ ።

፪ ወርእየ ክልኤተ አሕማረ ኀበ ውእቱ ሐይቅ ወወ
ረዱ እምኔሆን መሠግራን ይሕጽቡ መሣግሪሆሙ ።
፫ ወዓርገ ውስተ አሐቲ ሐመር እምኔሆን፡ ወይእቲ
ሐመር እንተ ስምዖን፡ ወይቤሎ ከመ ያርኁቃ ሕቀ
እምነ ምድር ከመ ይንበር ዲቤሃ ወይምሀር፡ ወነበረ
ውስተ ሐመር፡ ወመሀሮሙ ለሕዝብ ።
፬ ወሶበ ፈጸመ ነገሮ አርመመ፡ ወይቤሎ ለስምዖን
አእትቱ መንገለ ዕመቀ ባሕር፡ ወአውርዱ መሣግሪ
ክሙ ኀበ ይምነ ሐመር ።

፭ ወአውሥአ ስምዖን ወይቤሎ ሊቅ ሠራሕነ ኵላ
ሌሊተ እንዘ ናወርድ መሣግሪነ ወአልቦ ዘአኀዝነ፡
ወባሕቱ እስመ አዘዝከነ ናወርድ መሣግሪነ ።

፮ ወገቢሮሙ ከማሁ ተእኀዙ ብዙኃን ዓሣት ፈድፋደ
እስከ ይትበተክ መሣግሪሆሙ ።
፯ ወጸውዕዎሙ ለቢጾሙ እለ ውስተ ካልእ ሐመር
ከመ ይምጽኡ ወይርድእዎሙ፡ ወመጽኡ ወመልኡ
ክልኤሆን አሕማረ እስከ ይሰጠማ ።
፰ ወርእዮ ስምዖን ጴጥሮስ አስተብረከ ወሰገደ ኀበ
እገሪሁ ለእግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ ኅድገኒ እግዚኦ
ወሑር እምኔየ እስመ ብእሲ ኃጥእ አነ ።
፱ እስመ አኀዞ ድንጋፄ ወፍርሃት፡ ወኵሎሙ እለ ምስ
ሌሁ ደንገፁ በእንተ ዓሣት ዘተሠግሩ ።
፲ ወከማሁ ያዕቆብኒ ወዮሐንስ ደቂቀ ዘብዴዎስ አዕር
ክቲሁ ለስምዖን፡ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ለስም
ዖን፡ ኢትፍራህ እምይእዜሰ ሰብአ ታሤግር ።



ብዙ አጋንንትም አንተ የእግዚአብሔር ልጅ ክርስ ፵፩
ቶስ ነህ እያሉ እየጮኹ ይመጡ ነበር፡ ክርስቶስ
እንደሆነ ስላወቁት ይገሥፃቸው ነበር፡ ይህንንም እን
ዲናገሩ አይፈቅድላቸውም ነበር ። ማቴ ፰፡ ፳፱ ።
ማር ፫፡ ፲፪ ።
ሲነጋም ወጥቶ ወደ ምድረ በዳ ሄደ፡ ሕዝቡም እየ ፵፪
ፈለጉት ወደርሱ ሄዱና አልፎአቸው እንዳይሄድ
ይዘው አቆሙት ።
ለሌሎች ሀገሮች ደግሞ ስለ እግዚአብሔር መንግ ፵፫
ሥት እነግራቸው ዘንድ አለኝ፡ ስለዚህ ተልኬአለ
ሁና አላቸው ። ቀኍ ፲፰ - ፳ ። ምዕ ፰፡ ፩ ።
በገሊላ ምኵራቦችም ይሰብክ ነበር ። ቀኍ ፲፭ ። ፵፬

ምዕራፍ ፭፤

<u>ክፍል ፳፪፡ ስለ ስምዖን መጠራት ።</u>

ብዙ ሰዎችም ከእሱ ዘንድ ተሰብስበው የእግዚአብ ፩
ሔርን ቃል ይሰሙ ነበር፡ እሱ ግን በጌንሴሬጥ
ባሕር ወደብ ቆሞ ነበር ። ማቴ ፬፡ ፲፰ - ፳፪ ። ማር
፩፡ ፲፮ - ፲፰ ።
በዚያም ወደብ ሁለት መርከቦች ቆመው አየ፡ ከእነር ፪
ሱም ዓሣ አጥማጆቹ መረባቸውን ሊያጥቡ ወረዱ ።
ከሁለቱ ወደ አንዲቱ መርከብ ወጣ፡ ያችም መር ፫
ከብ የስምዖን ነበረች፡ በላይዋ ላይ ተቀምጦ ያስተ
ምር ዘንድ ከምድር ጥቂት እንዲያርቃት አዘዘው፡
በመርከብም ላይ ተቀምጦ ሕዝቡን አስተማራቸው ።
ትምህርቱን ከጨረሰ በኋላ ዝም አለ፡ ከዚህም በኋላ ፬
ስምዖንን ወደ ትልቁ ባሕር ፈቀቅ አድርጋችሁ በመ
ርከቡ በስተቀኝ በኩል መረባችሁን ጣሉ አለው ።
ዮሐ ፳፩፡ ፮ ።
ጴጥሮስም መልሶ መምህር! መረባችንን ስንጥል ፭
ሌሊቱን ሁሉ ደክመናል፡ የያዝነውም የለም፡ ነገር
ግን ስለ አዘዝከን መረባችንን እንጥላለን አለው ።
መዝ ፻፳፯፡ ፩ - ፪ ።
እንዳዘዛቸውም ባደረጉ ጊዜ መረቡ እስኪበጠስ ፮
ድረስ ብዙዎች ዓሣዎች ተያዙ ።
መጥተው ይረዱአቸውም ዘንድ በሌላ መርከብ ያሉ ፯
ትን ባልንጀሮቻቸውን ጠሩ፡ መጥተውም እስኪ
ጠልቁ ድረስ፡ ሁለቱን መርከቦች መሉ ። ቀኍ ፲ ።
ስምዖን ጴጥሮስም ይህን አይቶ ከጌታ እግር በታች ፰
ሰገደና አቤቱ! ይቅር በለኝ፡ ከእኔም ተለይ እኔ
ኃጢአተኛ ሰው ነኝና አለው ።
ፍርሃት ድንጋጤ ይዞታልና፡ ስለ ተያዙትም ዓሣዎች ፱
ከእሱ ጋር የነበሩት ሁሉ ደነገጡ ።
እንዲሁም የስምዖን ወዳጆች የዘብዴዎስ ልጆች ያዕ ፲
ቆብና ዮሐንስ ደነገጡ፡ ጌታ ኢየሱስም ስምዖንን
አትፍራ፡ ከእንግዲህ ወዲህስ ሰውን ታጠምዳለህ
አለው ። ኤር ፲፮፡ ፲፮ ። ማቴ ፲፫፡ ፵፯ ።

፲፩ ወአውፅኡ አሕማሬሆሙ ውስተ ምድር ወኀደጉ
ኵሎ ወተለውዎ ።

ክፍል ፳ወ፫ ፡ ዘከመ አሕየዎሙ እግዚእ ኢየሱስ
ለዘለምፅ ወለመፃጕዕ ።

፲፪ ወእንዘ ሀሎ ውስተ አሐቲ ሀገር መጽአ ብእሲ ዘለ
ምፅ ኵለንታሁ ፡ ወሶበ ርእዮ ለእግዚእ ኢየሱስ
ሰገደ ሎቱ በገጹ ፡ ወአስተብቍዖ ወይቤሎ ፡ እግዚኦ
እመሰ ፈቀድከ ትክል አንጽሖትየ ።
፲፫ ወሰፍሐ እዴሁ ወገሠሦ ወይቤሎ እፈቅድ ንጻሕ ፡
ወኃደጎ ለምጹ ሶቤሃ ።
፲፬ ወከልአ ኢይንግር ወኢለመኑሂ ፡ ወአዘዘ ወይቤሎ
ሑር ወአፍትን ርእሰከ ለካህን ወአብእ መበአከ ፡
በእንተ ዘነጻሕከ በከመ አዘዘ ሙሴ ከመ ይኩን
ስምዐ ላዕሌሆሙ ።
፲፭ ወተሰምዐ ነገሩ ፈድፋደ ፡ ወይመጽኡ ብዙኃን ሰብእ
ኀቤሁ ይሰምዕዎ ወይትፈወሱ እምደዌሆሙ ።

፲፮ ወውእቱሰ ይወፅእ ገዳመ ወይጼሊ በህየ ።

፲፯ ወእምዝ ኮነ በአሐቲ ዕለት እመዋዕል እንዘ ሀሎ
ይሜህሮሙ ወይነብሩ ፈሪሳውያን ወሊቃውንተ
ኦሪት እለ መጽኡ እምገሊላ ወእምኵሉ አህጉረ
ይሁዳ ወእምኢየሩሳሌም በኃይለ እግዚአብሔር
ውእቱ በዘይፌውስ ።

፲፰ ወአምጽኡ ኀቤሁ ብእሴ መፃጕዐ እንዘ ይፀውርዎ
አርባዕቱ እደው በዐራት ወፈቀዱ ያብእዎ ኀቤሁ
ይፈውሶ ።
፲፱ ወኃጥኡ እንተ ኀበ ያበውእዎ እስመ ጽፉቅ ሰብእ
ወዐርጉ ናሕሰ ወነሠቱ ጠፈረ ፡ ወአውረድዎ ምስለ
ዐራቱ ውስተ ቤት ቅድሜሁ ለእግዚእ ኢየሱስ ።

፳ ወርእዮ ሃይማኖቶሙ ይቤሎ ለውእቱ ብእሲ ተኃ
ድገ ለከ ኃጢአትከ ።
፳፩ ወአኃዙ የሐልዩ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን ወይበሉ ፡
ምንትኑ ውእቱ ዝንቱ ዘይነብብ ጽርፈተ ፡ መኑ ይክል
ኀዲገ ኃጢአት ዘእንበለ አሐዱ እግዚአብሔር በሕ
ቲቱ ።
፳፪ ወአእመሮሙ እግዚእ ኢየሱስ ዘይሔልዩ ወይቤ
ሎሙ ምንተኑ ትሔልዩ በልብክሙ ።
፳፫ ምንት ይቀልል እምብሂለ ተኃድገ ለከ ኃጢአትከ ፡
ወእምብሂለ ተንሥእ ወፀር ዐራተከ ወሑር ።
፳፬ ወከመ ታእምሩ ከመ ብዉሕ ሎቱ ለወልደ እጓለ
እመሕያው ይኅድግ ኃጢአተ በዲበ ምድር ፡ ወይ
ቤሎ ለውእቱ ድዉይ ለከ እብለከ ተንሥእ ወንሣእ
ዐራተከ ወእቱ ቤተከ ።



መርከቦቻቸውንም ወደ ምድር አወጡና ሁሉንም ፲፩
ትተው ተከተሉት ። ማቴ ፲፱ ፡ ፳፯ ።

ክፍል ፳፫ ፡ ጌታ ኢየሱስ
ለምፃሙንና ሽባውን እንዳዳነ ።

በአንዲት አገር ሳለም ሁለመናው ለምጽ የሆነ ሰው ፲፪
መጣ ፡ ጌታ ኢየሱስንም በየው ጊዜ በፊቱ ሰገደ
ለትና አቤቱ ! ብትወድስ ልታነፃኝ ትችላለህ ፡ እያለ
ማለደው ። ማቴ ፰ ፡ ፩ - ፬ ። ማር ፩ ፡ ፵ - ፵፭ ።
እጁንም ዘርግቶ ዳሠሠውና እወዳለሁ ንጻ አለው ፡ ፲፫
ወድያውኑም ለምጹ ለቀቀው ።
ለማንም ለማን እንዳይናገር ከለከለው ፡ ሂደህ ለካህን ፲፬
አስመርምር ፡ ስለ ነፃህም ሙሴ እንደ አዘዘ መበእህን
አቅርብ ፡ ብሎ አዘዘው ። ዘሌ ፲፬ ፡ ፪ ።

ዜናው በሁሉ ተዳረሰ ፡ ብዙ ሰዎችም ትምህርቱን ፲፭
ሊሰሙ ከደዌያቸው ሊፈወሱ ወደርሱ ይመጡ
ነበር ።
እርሱ ግን ወደ ምድረ በዳ እየወጣ በዚያ ይጸልይ ፲፮
ነበር ። ማር ፩ ፡ ፴፭ ።
ከዚህም በኋላ ከዕለታት በአንድ ቀን ፡ ከገሊላ ከይ ፲፯
ሁዳ አገሮችና ከኢየሩሳሌም የመጡ የኦሪት አዋቂ
ዎችና ፈሪሳውያን ተሰብስበው ሲያስተምራቸው
ሳለ ፡ የእግዚአብሔር ኃይል ሆነለት ፡ ይኸውም በሚ
ፈውስበት ጊዜ ነው ። ምዕ ፱ ፡ ፩ - ፰ ። ማር ፪ ፡
፩ - ፲፪ ። ምዕ ፯ ፡ ፲፯ ።
አራት ሰዎችም በአልጋ ተሸክመው ልምሾ የሆነ ፲፰
ውን ሰው ወደ እርሱ አመጡ ፡ እንዲፈውሰውም ወደ
እርሱ ሊያስገቡት ወደዱ ።
የሚያስገቡበትም አጡ ፡ ሰው ጽፍቅ ብሎ ነበርና ፲፱
ወደ ሰገነትም ወጥተው ጣራውን አፈረሱና ከነአል
ጋው ወደ ቤቱ ውስጥ አውርደው በጌታ ፊት
አኖሩት ።
ሃይማኖታቸውንም አይቶ ፡ ያንን ሰው ኃጢአትህ ፳
ተሠረየልህ አለው ።
ጻፎችና ፈሪሳውያንም የሚሳደብ ይህ ምንድነው ፡ ፳፩
ካንድ እግዚአብሔር ብቻ በቀር ኃጢአት ማስተሥ
ረይን ማን ይችላል ፡ ብለው ያስቡ ጀመር ። ኢሳ
፵፫ ፡ ፳፭ ።
ጌታ ኢየሱስም የሚያስቡትን አወቀባቸውና እን ፳፪
ዲህ አላቸው ፡ በልባችሁ ምን ታስባላችሁ ?
ኃጢአትህ ተሠረየልህ ከማለትና ፡ ተነሥተህ አልጋ ፳፫
ህን ተሸክመህ ሂድ ከማለት ምን ይቀላል ?
ለሰው ልጅ በምድር ላይ ኃጢአትን ያስተሠርይ ፳፬
ዘንድ ሥልጣን እንዳለው እንድታውቁ ፡ ያንንም
ድዉይ ተነሣና አልጋህን ተሸክመህ ወደ ቤትህ ግባ
ብዬሃለሁ አለው ።

፳፭ ወተንሥአ ሰቤሃ ወነሥአ ዐራቶ ዘዲቤሁ ይሰክብ በቅድሜሆሙ ፡ ወአተወ ቤቶ እንዘ ይሴብሖ ለእግዚአብሔር ።

፳፮ ወደንገፁ ኵሎሙ ወአእኰትዎ ለእግዚአብሔር ወፈርሁ ብዙኀ ፡ ወይቤሉ ርኢነ መንክረ ዮም ።

## ክፍል ፳ወ፱ ፡ በእንተ ሌዊ መጸብሐዊ ።

፳፯ ወእምዝ ወፂአ እምህየ ርእየ ብእሴ መጸብሐዌ ዘስሙ ሌዊ እንዘ ይነብር ኀበ ምጽባሕ ፡ ወይቤሎ ትልወኒ ።

፳፰ ወኀደገ ኵሎ ወተንሥአ ወተለዎ ። ።

፳፱ ወገብረ ሎቱ ሌዊ ዐቢየ ምሳሐ በቤቱ ወብዙኃን ሰብአ ምስሌሁ መጸብሐን ወኃጥአን እለ ረፈቁ ምስሌሆሙ ፡ ወባዕዳንሂ ብዙኃን ።

፴ ወአንጐርጐሩ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን ላዕሌሁ ፡ ወይቤልዎሙ ለአርዳኢሁ ለምንት ትበልዑ ወትሰትዩ ምስለ መጸብሐን ወኃጥአን ።

፴፩ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ ፡ ሕሙማን ይፈቅድዎ ለዐቃቤ ሥራይ ወአኮ ጥዑያን ።

፴፪ ኢመጻእኩ እጸውዕ ጻድቃነ ፡ አላ ኃጥአነ ለንስሐ ።

፴፫ ወይቤልዎ ለምንት አርዳኢሁ ለዮሐንስ ጽኑዐ ይጸውሙ ወጸሎተ ይገብሩ ፡ ወከማሁ እለሂ ፈሪሳውያን፡ ወአርዳኢከሰ እሊአከ ይበልዑ ወይሰትዩ ።

፴፬ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ኢይክሉ ደቂቀ ለመርዓዊ ጸዊመ እንዘ ሀሎ መርዓዊ ምስሌሆሙ ።

፴፭ ወባሕቱ ይመጽእ መዋዕል አመ ይነሥእዎ ለመርዓዊ እምኔሆሙ ፡ ወይእተ አሚረ ይጸውሙ ።

፴፮ ወይቤሎሙ በምሳሌ አልቦ ዘይጠቅብ፟ ግምደ ደርግሐ ልብስ ውስተ ስጠት ብሉይ ፡ ወእመ አኮሰ ይሰጥጦ ሐዲስ ለብሉይ ፡ ወምስለ ብሉይ ኢይዔሪ ።

፴፯ ወአልቦ ዘይወዲ ወይነ ሐዲስ ውስተ ዝቅ ብሉይ ፡ ወእመ አኮሰ ያነቅዖ ወወይኑኒ ይትከዐው ወዝቁኒ ይትኃጐል ።

፴፰ ወለወይንሰ ሐዲስ ውስተ ዝቅ ሐዲስ ይወድይዎ ፡ ወይትዐቀቡ በበይናቲሆሙ ።

፴፱ ወአልቦ ዘይሰቲ ጸዐፈ እንዘ ይፈቅድ ከራሜ ፡ እስመ ይኄይስ ጸዐፍ እምነ ከራሚ ።

ምዕራፍ ፮ ፤

## ክፍል ፳ወ፫ ፡ በእንተ ሰዊት ፡ ወዕለተ ሰንበት ።

፩ ወእምዝ ከዕበ ወፈረ እግዚእ ኢየሱስ እንተ ገራውህ በሰንበት ፡ ወመሐዉ አርዳኢሁ ሰዊተ ወሐሰዩ በእደዊሆሙ ወበልዑ ።



ያን ጊዜም ተነሥቶ ተኝቶበት የነበረውን አልጋ በፊታቸው ተሸክሞ ፡ እግዚአብሔርን እያመሰገነ ወደ ቤቱ ገባ ። ፳፭

ሁሉም ደነገጡና እግዚአብሔርንም አመሰገኑ ፡ እጅግም ፈሩ ፡ ዛሬ ድንቅ ነገርን አየን አሉ ። ፳፮

## ክፍል ፳፱ ፡ ስለ ቀራጩ ሌዊ ።

ከዚህም በኋላ ከዚያ ወጥቶ ሌዊ የሚባል ቀራጭ ሰው በግብር መቀበያው ቦታ አየና ፡ ተከተለኝ አለው ። ማቴ ፱ ፡ ፱ - ፲፫ ። ማር ፪ ፡ ፲፫ - ፲፯ ። ፳፯

ሁሉንም ተወና ተነሥቶ ተከተለው ። ፳፰

ሌዊም በቤቱ ታላቅ ምሳ አደረገለት ፡ ብዙ ሰዎችም ከእሱ ጋር ነበሩ ፡ ከነሱ ጋር ለምሳ ተቀምጠው ከነበሩትም ብዙዎች ቀራጮችና ኃጢአተኞች ነበሩ ፡ ሌሎችም ብዙዎች ነበሩ ። ምዕ ፲፭ ፡ ፩ ። ፳፱

ጻፎችና ፈሪሳውያን በሱ ላይ አንጐራጐሩ ፡ ደቀ መዛሙርቱንም ከቀራጮችና ከኃጢአተኞች ጋር ለምን ትበላላችሁ ትጠጣላችሁ ? አሏቸው ። ፴

ጌታ ኢየሱስም መልሶ እንዲህ አላቸው ፡ በሽተኞች ባለመድኃኒቱን ይፈልጉታል ፡ ጤነኞች ግን አይፈልጉትም ። ፴፩

ጻድቃንን ልጠራ አልመጣሁም ፡ ኃጥአንን ወደ ንስሐ ልጠራ ነው እንጂ ። ምዕ ፲፭ ፡ ፯ - ፲ ። ፴፪

እነሱም የዮሐንስ ደቀ መዛሙርት በእጅግ ይጾማሉ ፡ ጸሎትም ያደርጋሉ ፡ የፈሪሳውያን ወገኖች የሆኑትም እንዲሁ ያደርጋሉ ፡ ያንተ ደቀ መዛሙርቶች ግን ለምን ይበላሉ ይጠጣሉ? አሉት ። ማር ፪ ፡ ፲፰ - ፳፪ ። ፴፫

ጌታ ኢየሱስም እንዲህ አላቸው ፡ የሙሽራ ሚዜዎች ሙሽራ ከነሱ ጋር ሳለ መጾም አይችሉም ። ፴፬

ነገር ግን ሙሽራውን ከነሱ የሚወስዱበት ቀን ይመጣል ፡ ያን ጊዜም ይጾማሉ ። ፴፭

በምሳሌም እንዲህ አላቸው ፡ በአሮጌ ቀዳዳ ላይ የአዲስ ልብስ እራፊ የሚጥፍ የለም ፡ ያለዚያማ አዲሱ አሮጌውን ይቀደዋል ፡ ከአሮጌ ጋርም አንድ አይሆንም፤ ፴፮

ጉሽ ጠጅ በአሮጌ ረዋት የሚያኖር የለም ፡ ያለዚያማ ይሰነጥቀዋል ፡ ወይኑም ይፈስሳል ፡ ረዋቱም ይጐዳል። ፴፯

ጉሹን ጠጅ ግን በአዲስ ረዋት ይሾሙታል ፡ እርስ በርሳቸውም ይጠባበቃሉ ። ፴፰

አፍለኛውን ጠጅ ሊጠጣ ሲሻ ከምጣጣውን የሚጠጣ የለም ፡ ከከምጣጣው አፍለኛው ጠጅ ይሻላልና ። ፴፱

ምዕራፍ ፮ ፤

## ክፍል ፳፫ ፡ ስለ ሸትና ፡ ስለ ሰንበት ቀን ።

ከዚህም በኋላ ዳግመኛ ጌታ ኢየሱስ በሰንበት ቀን በእርሻ መካከል ሄደ ፡ ደቀ መዛሙርቱም ሸትን ቈርጠው በእጃቸው አሽተው በሉ ። ማቴ ፲፪ ፡ ፩ - ፰ ። ማር ፪ ፡ ፳፫ - ፳፰ ። ፩

፪ ወይቤልዎሙ ፈሪሳውያን ለምንት ትገብሩ ዘኢይከ
ውን ለገቢር በሰንበት ።
፫ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ ኢያንበብ
ክሙኑ ዘገብረ ዳዊት አመ ርኅበ ውእቱሂ ወእለ
ምስሌሁ ።
፬ ዘከመ ቦአ ቤተ እግዚአብሔር ወነሥአ ኅብስተ ቍር
ባን ዘይሠርዑ ፡ ወበልዐ ውእቱኒ ፡ ወወሀቦሙ ለእለ
ምስሌሁ ዘኢይከውኖሙ ለበሊዕ ፡ ዘእንበለ ለካህናት
ለባሕቲቶሙ ።
፭ ወይቤሎሙ እግዚኡ ውእቱ ለሰንበት ወልደ እጓለ
እመሕያው ።

## ክፍል ፳ወ፮ ፡ በእንተ ዘየብሰት እዴሁ ።

፮ ወእምዝ በካልእት ሰንበት ቦአ ምኵራበ ወመሀሮሙ፡
ወሀሎ ህየ ብእሲ ዘየብሰት እዴሁ እንተ የማን ።
፯ ወይትዐቀብዎ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን ለእመ ይፌ
ውሶ በሰንበት ከመ ይርከቡ ምክንያተ በዘያስተዋ
ድይዎ ።
፰ ወውእቱሰ የአምሮሙ ዘይሔልዩ ወይቤሎ ለውእቱ
ብእሲ ዘየብሰት እዴሁ ፡ ተንሥእ ወቁም ማእከለ ፡
ወተንሥአ ወቆመ ።
፱ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ እሴአለክሙ ዘይከውን
በሰንበት ፡ ገቢረ ሠናይኑ አው ገቢረ እኩይ ፡ አሕይዎ
ነፍስኑ ወሚመ ቀቲል ፡ ወአርመሙ ።
፲ ወነጺሮ ፡ ኵሎሙ በመዓት ፡ ይቤሎ ለውእቱ ብእሲ
ስፋሕ እዴከ ወሰፍሓ ፡ ወሐይወት እዴሁ ወኮነት
ከመ ካልእታ ።
፲፩ ወእሙንቱሰ ዐብዱ ፈድፋደ ፡ ወተማከሩ በበይናቲ
ሆሙ ዘከመ ይሬስይዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ።

## ክፍል ፳ወ፯ ፡ በእንተ ኅርዮቱ ሐዋርያት ።

፲፪ ወእምዝ ኮነ በውእቱ መዋዕል ፡ ዐርገ እግዚእ ኢየ
ሱስ ውስተ ደብር ይጸሊ ወያሌሊ በጸሎት ኀበ እግ
ዚአብሔር ።
፲፫ ወጸቢሖ ጸውዖሙ ለአርዳኢሁ ወኀረየ እምውስቴ
ቶሙ ዐሠርተ ወክልኤተ ፡ ወሰመዮሙ ሐዋርያተ ።
፲፬ እሉ እሙንቱ ስምዖን ዘተሰምየ ጴጥሮስ ፡ ወእንድ
ርያስ እኁሁ ፡ ወያዕቆብ ወዮሐንስ ፡ ወፊልጶስ ፡ ወበር
ተሎሜዎስ ።
፲፭ ወማቴዎስ ፡ ወቶማስ ፡ ወያዕቆብ ወልደ እልፍዮስ ፡
ወስምዖን ዘይብልዎ ቀናኢ ።
፲፮ ወይሁዳ ዘያዕቆብ ፡ ወይሁዳ አስቆሮታዊ ዘዐለዎ
ወዘአግብኦ ።

ፈሪሳውያንም በሰንበት ሊደረግ የማይገባውን ለምን ፪
ታደርጋላችሁ ? አሏቸው ። ዘፀ ፳ ፡ ፱ - ፲፪ ።
ጌታ ኢየሱስም መልሶ እንዲህ አላቸው ፡ እሱ በተ ፫
ራበ ጊዜ ከእሱ ጋር የነበሩም በተራቡ ጊዜ ፡ ዳዊት
ያደረገውን አላነበባችሁምን ? ፩ ሳሙ ፳፩ ፡ ፮ ።
ወደ ቤተ እግዚአብሔር ገብቶ የሠሩትን የመሥዋዕት ፬
ኅብስት ወስዶ እንደ በላ ፡ ለካህናት ብቻ እንጂ ፡ እነሱ
ሊበሉት የማይገባቸውንም አብረዉት ለነበሩ እንደ
ሰጣቸው ። ዘሌ ፳፬ ፡ ፰ - ፱ ።
የሰንበት ጌታዋ የሰው ልጅ ነው አላቸው ። ፭

## ክፍል ፳፮ ፡ እጁ ስለ ደረቀችው ሰው ።

ከዚህም በኋላ በሁለተኛዪቱ ሰንበት ወደ ምኵራቡ ፮
ገብቶ አስተማራቸው ፡ በዚያም ቀን እጁ የደረቀች
ሰው ነበረ ። ማቴ ፲፪ ፡ ፱ - ፲፬ ። ማር ፫ ፡ ፩ - ፮ ።
ጻፎችና ፈሪሳውያንም የሚከሱበትን ምክንያት ያገኙ ፯
ዘንድ በሰንበት ይፈውሰው እንደ ሆነ ብለው ይጠባ
በቁት ነበር ። ምዕ ፲፬ ፡ ፩ ።
እሱ ግን የሚያስቡትን ያውቀባቸው ነበርና እጁ የሰ ፰
ለለችውን ያንን ሰው ፡ ተነሥተህ በመካከል ቁም
አለው ፡ ተነሥቶም ቆመ ። ምዕ ፭ ፡ ፳፪ ።
ጌታ ኢየሱስም እጠይቃችኋለሁ ፡ በሰንበት ሊደረግ ፱
የሚገባው ምንድርነው ? መልካም ነው ወይስ ክፉ
ሥራ ? ነፍስ ማዳን ነው ወይስ መግደል ? አላቸው ፡
ዝም አሉ ።
ሁሉንም ከተመለከተ በኋላ ያንን ሰው እጅህን ዘርጋ ፲
አለው ፡ ሰውዬውም ዘረጋት ፡ እጁም ዳነችና እንደ
ሁለተኛዪቱ፤ሆነች ። ፩ ነገ ፲፫ ፡ ፮ ።
እነሱ ግን እጅግ ተቈጡ ፡ ጌታ ኢየሱስን ምን እንደ ፲፩
ሚያደርጉት እርስ በርሳቸው ተማከሩ ።

## ክፍል ፳፯ ፡ ሐዋርያትን ስለ መምረጡ ።

ከዚህም በኋላ በዚያ ቀን እንዲህ ሆነ ፡ ጌታ ኢየሱስ ፲፪
ሊጸልይ ወደ ተራራ ወጣ ፡ ወደ እግዚአብሔርም
በጸሎት ይማልድ ነበር ። ማቴ ፲፬ ፡ ፳፮ ። ማር ፫ ፡
፲፫ - ፲፱ ።
ሲነጋም ደቀ መዛሙርቱን ጠራቸውና ከውስጣቸው ፲፫
አሥራ ሁለቱን መረጠ ፡ ሐዋርያትም ብሎ ሰየማ
ቸው ። ማቴ ፲ ፡ ፩ ።
እነሱም እነዚህ ናቸው ፡ ጴጥሮስ የተባለው ስምዖን ፡ ፲፬
ወንድሙ እንድርያስም ፡ ያዕቆብና ዮሐንስ ፡ ፊልጶስና
በርተሎሜዎስ ።
ማቴዎስና ቶማስ ፡ የእልፍዮስ ልጅ ያዕቆብ ፡ ቀናተኛ ፲፭
የሚባለው ስምዖን ።
የያዕቆብ ወንድም ይሁዳና ፡ ከድቶ ያስያዘው ያስቆ ፲፮
ሮቱ ሰው ይሁዳ ።

፲፯ ወወረደ ምስሌሆሙ ወቆመ በገዳም ፡ ወብዙኃን ሰብእ
እምአርዳኢሁ ፡ ወብዙኃን ጥቀ እምሕዝብ ዘእም
ኵሉ ይሁዳ ፡ ወእምኢየሩሳሌም ፡ ወእምጺራልያስ ፡
ወጺራልዩ ፡ ወእምጢሮስ ወሲዶና ፡ እለ መጽኡ ይስ
ምዕዎ ወይትፈወሱ እምደዌሆሙ ።

፲፰ ወእለሂ አጋንንት እኩያን የሐይዉ ።

፲፱ ወኵሎሙ አሕዛብ ይፈቅዱ ይግሥሥዎ እስመ ኃይል
ይወፅእ እምኔሁ ወያሐይዎሙ ለኵሎሙ ።

ክፍል ፳ወ፰ ፡ በእንተ ስብከቱ በውስተ ደብር ።

፳ ወውእቱሰ አንሥአ አዕይንቲሁ ኀበ አርዳኢሁ ወይ
ቤሎሙ ፡ ብፁዓን አንትሙ ነዳያን እስመ ለክሙ
ይእቲ መንግሥተ እግዚአብሔር ።

፳፩ ብፁዓን እለ ትርኅቡ ይእዜ እስመ ትጸግቡ ፡ ብፁዓን
እለ ትበክዩ ይእዜ እስመ ትስሕቁ ።

፳፪ ብፁዓን አንትሙ ሶበ ይጸልኡክሙ ሰብእ ወይፈል
ጡክሙ ወይሰድዱክሙ ወይጼእሉክሙ ወያወፅኡ
ለክሙ ስመ እኩየ በእንተ ወልደ እጓለ እመሕያው ።

፳፫ ተፈሥሑ ወተኃሠዩ ይእተ አሚረ ወአንፈርዕፁ
እስመ ብዙኅ ዕሤትክሙ በሰማያት ፡ እስመ ከማሁ
ረሰይዎሙ ለነቢያት ቀደምት አበዊሆሙ ።

፳፬ ወባሕቱ አሌ ለክሙ አብዕልት እስመ ሠለጥክሙ
ትፍሥሕተክሙ ።

፳፭ አሌ ለክሙ እለ ትጸግቡ ይእዜ እስመ ትርኅቡ ፡
አሌ ለክሙ እለ ትስሕቁ ይእዜ እስመ ትበክዩ ወት
ላሕዉ ።

፳፮ አሌ ለክሙ ሶበ ሠናየ ይብል ሰብእ ላዕሌክሙ ወይ
ዌድሱክሙ እስመ ከማሁ ረሰይዎሙ ለነቢያተ ሐሰት
አበዊሆሙ ።

፳፯ ወለክሙሰ እለ ትሰምዑኒ እብለክሙ አፍቅሩ ጸላእ
ተክሙ ፡ ወግበሩ ሠናየ ለእለ ይፀርሩክሙ ።

፳፰ ወደኃርዎሙ ለእለ ይረግሙክሙ ፡ ወጸልዩ ለእለ
ይትዔገሉክሙ ።

፳፱ ወለዘሂ ጸፍዐከ መልታሕቴከ መጥዎ ካልእታሂ ፡ ወለ
ዘኒ ነሥአከ ልብሰከ ክዳነከሂ ኢትክልኦ ።

፴ ለኵሉ ዘሰአለከ ሀብ ፡ ወለዘኒ ኄደከ ንዋየከ ኢትኅ
ሥሦ ።

፴፩ ወበከመ ትፈቅዱ ይግበሩ ለክሙ ሰብእ ከማሁ ግበሩ
ሎሙ አንትሙኒ ።

የሉቃስ ወንጌል ፮ ።

ከነርሱም ጋር ወርዶ በሰፊ ቦታ ተቀመጠ ፡ ከደቀ ፲፯
መዛሙርቱም ወገን ብዙ ሰዎች ነበሩ ፡ ከመላው
ይሁዳ ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ከየገጠሩ ፡ ከየመንደሩ ፡ ከጢ
ሮስና ከሲዶና ፡ ትምህርቱን ሊሰሙ ከደዌያቸውም
ሊፈወሱ የመጡት ከሕዝቡ ወገን እጅግ ብዙዎች
ነበሩ ። ማር ፫ ፡ ፯ - ፲ ።
ከሩዎች አጋንንት ያደሩባቸውም ይድኑ ነበር ። ማቴ ፲፰
፬ ፡ ፳፭ ።
ሕዝቡ ሁሉ ሊዳሥሡት ይሹ ነበር ፡ ኀይል ከርሱ ፲፱
ይወጣ ነበርና ፡ ሁሉንም ይፈውሳቸው ነበረ ።

ክፍል ፳፰ ፡ በተራራ ስለ ማስተማሩ ።

እርሱም ዓይኖቹን ወደ ደቀ መዛሙርቱ አንሥቶ ፳
እንዲህ አላቸው ፡ እናንተ ድኾች ብፁዓን ናችሁ ፡
የእግዚአብሔር መንግሥት የእናንተ ናትና ። ማቴ
፭ ፡ ፫ - ፵፰ ።
ዛሬ የምትራቡ ብፁዓን ናችሁ ትጠግባላችሁና ፡ ዛሬ ፳፩
የምታለቅሱ ንኡዳን ናችሁ ደስ ይላችኋልና ። ራእ
ዮሐ ፯ ፡ ፲፯ ። መዝ ፻፳፮ ፡ ፭ - ፮ ። ኢሳ ፳፩ ፡ ፫ ።
ሰዎች ስለ ሰው ልጅ ብለው ቢጠሏችሁ ከሰው ለይ ፳፪
ተው ቢያሳድዷችሁ ፡ ቢሰድቧችሁ ፡ ክፉ ስምም
ቢያወጡላችሁ ንኡዳን ናችሁ ። ዮሐ ፲፮ ፡ ፪ ።
ያን ጊዜ ፈጽሞ ደስ ይበላችሁ ዕልል በሉ ፡ ዋጋ ፳፫
ችሁ በሰማይ ብዙ ነውና ፡ የቀደሙ አባቶቻቸው
ነቢያትን እንዲሁ ያደርጉዋቸው ነበርና ። ማቴ
፳፫ ፡ ፴፬ ።
ነገር ግን ባለጸጎች ፡ ወዮላችሁ ተድላ ደስታችሁን ፳፬
ፈጽማችኋልና ። ያዕ ፭ ፡ ፩ - ፭ ።
ዛሬ የምትጠግቡ ወዮላችሁ ትራባላችሁና ፡ ዛሬ የም ፳፭
ትስቁ ወዮላችሁ ታዝናላችሁ ታለቅሳላችሁና ።
ኢሳ ፭ ፡ ፳፪ ። ፳፭ ፡ ፲፭ ። ያዕ ፬ ፡ ፱ ።
ሰው ስለ እናንተ መልካሙን ነገር ቢናገርላችሁ ፡ ፳፮
ቢያመሰግኑዋችሁ ወዮላችሁ ፡ አባቶቻቸውም ለሐ
ሰት ነቢያት እንዲሁ ያደርጉላቸው ነበርና ። ሚክ
፪ ፡ ፲፩ ። ያዕ ፬ ፡ ፬ ።
ለምትሰሙኝ ለእናንተ ግን እንዲህ እላችኋለሁ ፡ ፳፯
"ጠላቶቻችሁን ውደዱ ፡ ለሚጠሏችሁም መልካም
አድርጉ" ። ዘፀ ፳፫ ፡ ፬ ።
የሚረግሟችሁን መርቁአቸው ፡ ለሚበድሏችሁም ፳፰
ጸልዩላቸው ። ምዕ ፳፫ ፡ ፴፬ ።
ጉንጭህን ለሚመታህ ሁለተኛዪቱንም ስጠው ፡ ፳፱
መጐናጸፊያህን ለወሰደብህ ቀሚስህንም አትከል
ክለው ።
ለለመነህ ሁሉ ስጥ ፡ ገንዘብህን የወሰደውንም የሚ ፴
ቀማህንም አትከታተለው ። ዘዳ ፲፭ ፡ ፯ - ፰ ።
ሰዎች ሊያደርጉላችሁ እንደምትወዱትም ፡ እናን ፴፩
ተም እንዲሁ አድርጉላቸው ። ማቴ ፯ ፡ ፲፪ ።

፴፪ ወእመሰ ዳእሙ ዘአፍቀረክሙ አፍቀርክሙ ምንትኑ
እንከ ዕሤትክሙ ኃጥአንሂ ዘሰ ይገብሩ፡ ዘያፈቅሮሙ
ያፈቅሩ ።
፴፫ ወእመኒ አሠነይክሙ ለእለ ያሤንዩ ለክሙ ምንትኑ
እንከ ዕሤትክሙ፡ ኃጥአንሂ ከማሁሰ ይገብሩ ።
፴፬ ወእመኒ ለቃሕክሙ እምኀበ ዘትሴፈዉ ትትፈደዩ
እምኔሁ፣ ምንትኑ እንከ ዕሤትክሙ ኃጥአንሂ ይሌቅ
ሕዎሙ ለኃጥአን ከመ ይትፈደይዎሙ ዕሩየ ።

፴፭ ወይእዜኒ አፍቅሩ ጸላእትክሙ፡ ወአሠንዩ ሎሙ፡
ወለቅሑ እንዘ ኢትሴፈዉ ትትፈደዩ፣ ወይከውን
ብዙኀ ዕሤትክሙ፡ ወትከውኑ ወሉደ ለልዑል፡
እስመ ውእቱ ኄር ላዕለ ኄራን ወላዕለ እኩያን ።

፴፮ ወኩኑ መሐርያነ ከመ አቡክሙ ሰማያዊ መሐሪ
ውእቱ ።
፴፯ ኢትኰንኑ ወኢትትኰነኑ፡ ወኢትግፍዑ ወኢይግ
ፍዑክሙ፡ ኅድጉ ወየኀድጉ ለክሙ ።

፴፰ ሀቡ ወይትወሀበክሙ መሥፈርተ ሠናየ ንሕኑሐ
ወምሉአ ወዝሕዙኀ ይሁቡክሙ ውስተ ሕፅንክሙ፡
ወበመሥፈርት ዘሠፈርክሙ ይሠፍሩ ለክሙ ።



የሚወዷችሁን ብቻ ብትወዱማ እንግዲህ ዋጋችሁ ፴፪
ምንድር ነው? ይህንስ ኃጥአንም ያደርጋሉ፡ የሚወ
ዷቸውን ይወዳሉና ።
በጎ ለሚያደርጉላችሁ በጎ ብታደርጉ እንግዲህ ዋጋ ፴፫
ችሁ ምንድርነው? እንዲህስ ኃጥአንም ያደርጋሉ ።
እንዲከፍላችሁ ተስፋ ለምታደርጉት ብታበድሩ፣ እን ፴፬
ግዲህ ዋጋችሁ ምንድር ነው? ኃጥአንም በአበደሩት
ልክ ይከፍሏቸው ዘንድ ለኃጥአን ያበድሯቸዋልና ።
ዘሌ ፳፭ ፡ ፴፭ - ፴፯ ።
አሁንም ጠላቶቻችሁን ውደዱ፡ መልካምም አድር ፴፭
ጉላቸው፡ ልትከፈሉ ተስፋ ሳታደርጉ አበድሩ፣ ዋጋ
ችሁም ብዙ ይሆናል፡ የልዑል እግዚአብሔርም
ልጆች ትሆናላችሁ፡ እሱ ለደጎችም ለክፉዎችም
ቸር ነውና ።
ሰማያዊ አባታችሁ ርኅሩኅ እንደሆነ፣ እናንተም የም ፴፮
ትራሩ ሁኑ ። ማቴ ፭ ፡ ፵፪ ። ማር ፬ ፡ ፳፬ ።
አትፍረዱ አይፈረድባችሁ፡ አትበድሉ አይበድሏ ፴፯
ችሁ፡ ይቅር በሉ ይቅር ይሏችኋል ። ሮሜ ፲፬ ፡
፱ - ፲ ። ማቴ ፯ ፡ ፲፬ ። ፯ ፡ ፩ ።
ስጡ ይሰጣችኋል፡ የበዛ፣ የሞላ፡ የተትረፈረፈ በመ ፴፰
ልካም መሥፈሪያ ሠፍረው ይሰጧችኋል፡ በሠፈራ
ችሁትም መሥፈሪያ ይሠፍሩላችኋል ። ማቴ ፯ ፡ ፪ ።
ማር፬ ፡ ፳፬ ።

ክፍል ፳ወ፱ ፡ በእንተ ክልኤት ትእዛዛት ።

፴፱ ወመሰለ ሎሙ ወይቤሎሙ ይክልኑ ዕዉር ለዕዉር
መሪሐቶ፡ አኮኑ ክልኤሆሙ ይወድቁ ውስተ ግብ ።

፵ አልቦ ረድእ ዘየዓቢ እምሊቁ፡ መጠኑ ለኵሉ ይኩን
ከመ ሊቁ ።

፵፩ ምንተኑ ትኔጽር ኃሠረ ዘውስተ ዓይነ ቢጽከ፣ ወኢ
ትሬኢ ሠርዌ ዘውስተ ዐይንከ ።

፵፪ ወእፎ ትክል ብሂሎቶ ለቢጽከ ተዐገሥ እኁየ አው
ፅእ ኃሠረ እምዐይንከ ወአንተሰ ኢትሬኢ ሠርዌ
ዘውስተ ዐይንከ፣ አ መደልው አውፅእ ቅድመ ሠርዌ
እምዐይንከ ወእምዝ ትኔጽር ታውፅእ ኃሠረ እምዐ
ይነ ቢጽከ ።

፵፫ አልቦ ዕፅ ሠናይ ዝይፈሪ ፍሬ እኩየ፡ ወአልቦ ዕፅ
እኩይ ዘይፈሪ ፍሬ ሠናየ ።

፵፬ ወኵሉ ዕፅ እምፍሬሁ ይትዐወቅ፣ ወኢየአርሩ በለሰ
እምአሥዋክ፡ ወኢይቀስሙ አስካለ እምአሜከላ ።
፵፭ ኄር ብእሲ እምሠናይ መዝገበ ልቡ ያወፅእ ለሠና

ክፍል ፳፱ ፡ ስለ ሌሎች ትእዛዛት ።

ምሳሌም መሰለላቸውና እንዲህ አላቸው፣ ዕዉር ፴፱
ዕዉርን ሊመራው ይችላልን? ሁለቱስ ከጉድጓድ
ውስጥ ይወድቁ የለምን? ማቴ ፲፭ ፡ ፲፬ ።
ከመምህሩ የሚበልጥ ደቀ መዝሙር የለም፡ ለሁ ፵
ሉም መጠኑ እንደ መምህሩ ይሁን ። ማቴ ፲
፳፬ - ፳፭ ። ዮሐ ፲፭ ፡ ፳ ።
በወንድምህ ዐይን ውስጥ ያለውን ጉድፍ ታያለህ፣ ፵፩
በዐይንህ ውስጥ ያለውን ስንጣሪ ግን ለምን አታ
ይም ። ማቴ ፯ ፡ ፫ ።
ወንድምህንም፣ ወንድሜ ሆይ! ታገሥ በዐይንህ ፵፪
ውስጥ ያለውን ጉድፍ ላውጣልህ ልትለው እንደ
ምን ትችላለህ? አንተ ግን በዐይንህ ውስጥ ያለውን
ጉድፍ አታይም፡ አንተ ግብዝ አስቀድሞ ከዐይንህ
ስንጣሪውን አውጣ፡ ከዚህ በኋላ በባልንጀራህ ዐይን
ውስጥ ያለውን ጉድፍ ታወጣ ዘንድ ታያለህ ።
ክፉ ፍሬን የሚያፈራ መልካም ዛፍ የለም፡ መል ፵፫
ካም ፍሬ የሚያፈራ ክፉ ዕንጨትም የለም ። ማቴ
፲፪ ፡ ፴፪ - ፴፬ ።
ዛፍ ሁሉ ከፍሬው ይታወቃል፣ ከእሾኽ በለስን አይ ፵፬
ለቅሙም፣ ከደንደርም ወይንን አይለቅሙም ።
መልካም ሰው ከመልካም ልቡ መዝገብ መልካምን ፵፭

ይት ፡ ወእኩይሰ ብእሲ እምእኩይ መዝገበ ልቡ ያወ
ፅአ ለእኪት ፡ እስመ እምተረፈ ልብ ይነብብ አፍ ።

፵፮ ለምንት እንከ ትብሉኒ እግዚኦ እግዚኦ ወኢትገብሩ
ዘአቤለክሙ ።
፵፯ ኵሉ ዘይመጽእ ኀቤየ ወይሰምዐኒ ቃልየ ወይገብሮ
አርእየክሙ ዘይመስል ።
፵፰ ይመስል ብእሴ ጠቢበ ዘሐነጸ ቤቶ ወከረየ ወአዕ
መቀ ወሣረረ መሠረቶ ዲበ ኰኵሕ ፡ ወብዙኃን አፍ
ላግ ገፍዕዎ ወኀይዝት መጺአሙ ለውእቱ ቤት ወስ
እኑ አንቀልቅሎቶ ፡ እስመ ዲበ ኰኵሕ ተሣረረ ።
፵፱ ወዘሰ ይሰምዐኒ ቃልየ ወኢይገብሮ ፡ ይመስል ብእሴ
ዘሐነጸ ቤቶ መልዕልተ ምድር ዘእንበለ መሠረት ፡ ወገ
ፍዕዎ ወኃይዝት ወወድቀ ሶቤሃ ወኮነ ድቀቱ ለው
እቱ ቤት ዐቢየ ።

ምዕራፍ ፯ ፤

<u>ክፍል ፴ ፡ በእንተ ወዓሊ ዘመስፍን ።</u>

፩ ወፈጺሞ ነጊሮቶሙ ቃሎ ለሕዝብ ቦአ ቅፍርናሆም ።

፪ ወሀሎ አሐዱ መስፍን ወገብሩ ይደዊ ወአልጸቀ
ይሙት ወክቡር ውእቱ በኀቤሁ ።
፫ ወሰሚዖ በእንተ እግዚእ ኢየሱስ ለአከ ኀቤሁ ረበ
ናተ አይሁድ ያስተብቍዕዎ ከመ ይምጻእ ወያሕዩ
ሎቱ ቍልዔሁ ።
፬ ወመጽኡ ኀበ እግዚእ ኢየሱስ ወአስተብቍዕዎ ወይ
ቤልዎ ፍጡነ ረድ እስመ ይደልዎ ትግበር ምስሌሁ
ዘንተ ።
፭ እስመ ያፈቅር ሕዝበነ ፡ ወምኵራበነኒ ውእቱ ሐነጸ
ለነ ።
፮ ወሖረ እግዚእ ኢየሱስ ምስሌሆሙ ወአልጺቆ ኀበ
ቤቱ ለአከ አዕርክቲሁ ውእቱ መስፍን ኀቤሁ እንዘ
ይብል ፡ እግዚኦ ኢትፃሙ እስመ ኢይደልወኒ ከመ
ትባእ ታሕተ ጠፈረ ቤትየ ።
፯ ወለልየኒ ኢይደልወኒ እምጻእ ኀቤከ ፡ ወባሕቱ
አዝዝ በቃልከ ወየሐዩ ቍልዔየ ።
፰ እስመ አነሂ ብእሲ መኰንን አነ ወብየ ወዐልት ፡ ወእ
ብሎ ለዝ ሑር ወየሐውር ፡ ወለካልኡኒ ነዓ ወይመ
ጽእ ፡ ወለገብርየኒ ግበር ከመዝ ወይገብር ።
፱ ወሰሚዖ እግዚእ ኢየሱስ ዘንተ እምኔሁ አንከሮ
ወተመይጦ ይቤሎሙ ለሕዝብ እለ ተለውዎ ፡ ኢረ
ከብኩ ዘከመዝ ዘይትአመን በውስተ እስራኤል ።

፲ ወአተዉ እለ ተፈነዉ ረከብዎ ለገብሩ በዘሐይወ ።



ያወጣል ፡ ክፉ ሰውም ከክፉ ልቡ መዝገብ ክፉ ነገ
ርን ያወጣል ፡ ከልብ የተረፈውን አንደበት ይና
ገራልና ።
እንግዲህ አቤቱ አቤቱ ትሉኛላችሁ የምላችሁን ፵፮
አታደርጉም ። ሚል ፩ ፡ ፯ ። ማቴ ፳፫ ፡ ፲፩ - ፲፪ ።
ወደ እኔ የሚመጣና ቃሌን ሰምቶ የሚፈጽመው ፡ ፵፯
የሚመስለውን አሳያችኋለሁ ።
መሠረቱን አጥልቆ ቈፍሮ መሥርቶ ቤቱን በአለት ፵፰
ላይ የሠራ ብልህ ሰውን ይመስላል ፡ ብዙ ፈሳሾች
ወንዞች መጥተው ያን ቤት ገፉት ሊያነዋውጡ
ትም አልቻሉም ፡ በአለት ላይ ተሠርቷልና ።
ቃሌን ሰምቶ የማይሠራው ሰው ፡ ቤቱን ያለ መሠ ፵፱
ረት በምድር ላይ የሠራ ሰውን ይመስላል ፡ ጐር
ፎች ገፉት ወዲያውኑም ወደቀ ፡ የዚያም ቤት አወ
ዳደቁ ታላቅ ሆነ ።

ምዕራፍ ፯ ፤

<u>ክፍል ፴ ፡ ስለ መስፍኑ ሎሌ ።</u>

ለሕዝቡም ትምህርቱን ነግሮ ከፈጸመ በኋላ ወደ ፩
ቅፍርናሆም ገባ ።ማቴ ፰ ፡ ፭ - ፲፫ ።
አንድ መስፍንም ነበረ ፡ ባርያውም ታሞ ሊሞት ፪
ቀርቦ ነበር ፡ እሱም ባለሟሉ ነበር ።
የጌታ ኢየሱስን ነገር በሰማ ጊዜ መጥቶ አገልጋዩን ፫
እንዲያድንለት ይማልዱት ዘንድ የአይሁድን ሽማ
ግሎች ወደርሱ ላከ ።
ወደ ጌታ ኢየሱስም መጡና ይህን ልታደርግለት ፬
ይገባዋልና ፈጥነህ ውረድ ብለው ማለዱት ።

ወገናችንን ይወዳልና ፡ ምኵራባችንንም እርሱ ሠር ፭
ቶልናልና ።
ጌታ ኢየሱስም ከነርሱ ጋር ሄደ ወደ ቤቱም በቀ ፮
ረበ ጊዜ ፡ ያ መስፍን ወዳጆቹን ላከ እንዲህ ብሎ ፡
አቤቱ ! አትድከም ከቤቴ ጣራ በታች ልትገባ አይ
ገባኝምና ። ምዕ ፲፭ ፡ ፲፱ ። ዘፍ ፴፪ ፡ ፲ ።
እኔም ወዳንተ ልመጣ አይገባኝም ፡ ነገር ግን በቃ ፯
ልህ እዘዝ ፡ ብላቴናዬም ይድናል አለው ።
እኔም እኮ ገዥ ሰው ነኝ ፡ ሎሌዎችም አሉኝ ይህን ፰
ሂድ ብለው ይሄዳል ፡ ሌላውንም ና ብለው ይመጣል ፡
አገልጋዬንም እንዲህ አድርግ ብለው ያደርጋል ።
ጌታ ኢየሱስም ይህን ከእሱ በሰማ ጊዜ አደነቀው ፡ ፱
መለስ ብሎም ይከተሉት ለነበሩት ሕዝብ ፡ በእስራ
ኤል መካከል እንኳ እንዲህ ያለ ሃይማኖት ያለው
ሰው አላገኘሁም አላቸው ።
የተላኩትም በተመለሱ ጊዜ ብላቴናውን ድኖ አገ ፲
ኙት ።

## ክፍል ፴ወ፩ ፡ በእንተ ወልደ መበለት ።

፲፩ ወበሳኒታ ሖረ ሀገረ እንተ ስማ ናይን ፡ ወሖሩ ምስ
ሌሁ አርዳኢሁ ወሕዝብኒ ብዙኅ ።
፲፪ ወበጺሖ ኀበ አንቀጸ ሀገር ረከበ ቀበረ ሰዉረ ዘወ
ልደ ብእሲት መበለት ዘውእቱ አሐዱ ለእሙ ወብ
ዙኃን ሰብአ ሀገር ምስሌሃ ።
፲፫ ወሶበ ርእያ እግዚእነ ፡ መሐራ ወተሣሀላ ፡ ወይቤላ
ኢትብክዪ ።
፲፬ ወቀርበ ወአኀዘ ነፍቆ ወቆሙ እለ ይፀውርዎ ፡ ወይ
ቤሎ ለከ እብለከ ወሬዛ ተንሥእ ።
፲፭ ወተንሥአ ወነበረ ውእቱ በድን ወተናገረ ርቱዐ
ወአወፈዮ ለእሙ ።
፲፮ ወፈርሁ ኵሎሙ ወሰብሕዎ ለእግዚአብሔር ወይ
ቤሉ ዓቢይ ነቢይ ተንሥአ ለነ ወተሣሀሎሙ እግዚ
አብሔር ለሕዝቡ ።
፲፯ ወተሰምዐ ዝንቱ ነገር በኵሉ በሐውርተ ይሁዳ ወበ
ኵሉ አድያሚሃ ።

## ክፍል ፴ወ፪ ፡ በእንተ እለ ተፈነዉ እምኀበ ዮሐንስ ።

፲፰ ወነገርዎ አርዳኢሁ ለዮሐንስ ዘንተ ኵሎ ።
፲፱ ወጸውዐ ዮሐንስ ክልኤተ እምአርዳኢሁ ወለአኮሙ
ኀበ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤ ፡ አንተኑአ ዘይመጽእ
ወሚመ ቦኑ ካልእ ዘንሴፎ ።
፳ ወበጺሖሙ እለ ለአኮሙ ኀቤሁ ይቤልዎ ፡ ዮሐንስ
መጥምቅ ለአከነ ኀቤከ ወይቤ ፡ አንተኑአ ዘይመጽእ
ወቦኑ ካልእ ዘንሴፎ ።
፳፩ ወፈወሶሙ ለብዙኃን ሶቤሃ እምደዌሆሙ ወእምሕ
ማሞሙ ወእምአጋንንት እኩያን ወለብዙኃን ዕው
ራን ጸገዎሙ ብርሃነ ይርአዩ ።
፳፪ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ ሑሩ ንግ
ርዎ ለዮሐንስ ዘሰማዕክሙ ወዘርኢክሙ ፡ ዕዉራን
ይሬእዩ ፡ ወሐንካሳን የሐውሩ ፡ ወእለ ለምጽ ይነጽሑ ፡
ወጽሙማን ይሰምዑ ፤ ወምዉታን ይትነሥኡ ፤ ወነዳ
ያን ይዜነዉ ወይትፌሥሑ ።
፳፫ ወብፁዓን እለ ኢይትዐቀፉ ብየ ።

## ክፍል ፴ወ፫ ፡ በእንተ ወድሶቱ ዮሐንስሃ መጥምቀ ።

፳፬ ወኃሊፎሙ አርዳኢሁ ለዮሐንስ አንዘ ይበሎሙ
ለሕዝብ በእንተ ዮሐንስ መጥምቅ ፡ ምንተኑ ወፃእ
ክሙ ገዳመ ትርአዩ ፡ ብርዐኑ ዘይትሐወስ እምነፋስ ።
፳፭ ወምንተኑመ ወፃእክሙ ትርአዩ ፡ ብእሴኑ ዘርሡይ በቀ
ጠንት አልባስ ፡ ናሁ እለሰ ርሡያን አልባሰ ክብር
ውስተ አብያተ ነገሥት ሀለዉ ።

## ክፍል ፴፩ ፡ ስለ መበለቲቱ ልጅ ።

በማግሥቱም ናይን ወደምትባል አገር ሄደ ፡ ደቀ ፲፩
መዛሙርቱም ብዙ ሕዝብም አብረዉት ሄዱ ።
ወደ ከተማው በር በደረሰ ጊዜ ፡ ያንዲት መበለት ፲፪
ሴት ልጅ ሬሳ ተሸክመው አገኘ ፡ ይኸውም ለእናቱ
አንድ የነበረ ነው ፡ ብዙዎችም የከተማው ሰዎች
አብረዋት ነበሩ ። ፩ ነገ ፲፯ ፡ ፲፯ ። ኤር ፯ ፡ ፳፮ ።
ጌታችንም ባያት ጊዜ አዘነላት ፡ ራራላት ፡ አታል ፲፫
ቅሽም አላት ። ምዕ ፰ ፡ ፶፪ ።
ቀረብ ብሎም ቃሬዛውን ያዘ ፡ የተሸከሙትም ቆሙ ፡ ፲፬
እሱንም አንተ ጐበዝ ተነሥ እልሃለሁ አለው ።
ያም ሬሳ ተነሥቶ ተቀመጠ ፡ አቃንቶም ተናገረ ፡ ፲፭
ለእናቱም ሰጠው ። ፩ ነገ ፲፯ ፡ ፳፫ ።
ሁሉም ፈሩ እግዚአብሔርንም አመሰገኑት ፡ ታላቅ ፲፮
ነቢይ ተነሣልን ፡ እግዚአብሔርም ሕዝቡን ይቅር
አለ እያሉ ። ምዕ ፩ ፡ ፷፰ ። ዘዳ ፲፰ ፡ ፲፭ ። ዮሐ ፬ ፡ ፲፱ ።
ይህም ነገር በይሁዳ አገሮች ሁሉና በአውራጃዋም ፲፯
ሁሉ ተሰማ ።

## ክፍል ፴፪ ፡ ከዮሐንስ ስለ ተላኩት መልእክተኞች ።

ደቀ መዛሙርቱም ይህን ሁሉ ለዮሐንስ ነገሩት ። ፲፰
ማቴ ፲፩ ፡ ፪-፲፱ ።
ዮሐንስም ከደቀ መዛሙርቱ ሁለቱን ጠርቶ የሚመ ፲፱
ጣው አንተ ነህን ? ወይስ ተስፋ የምናደርገው ሌላ
አለ ? ብሎ ወደ ጌታ ኢየሱስ ላካቸው ።
የላካቸውም ወደርሱ ደርሰው ፡ መጥምቁ ዮሐንስ ፳
የሚመጣው አንተ ነህን ወይስ ተስፋ የምናደርገው
ሌላ አለ ? ብሎ ወዳንተ ልኮናል አሉት ።
ያን ጊዜም ብዙዎችን ከደዌአቸው ከሕመማቸው ፳፩
ከክፉዎች አጋንንትም ፈወሳቸው ፡ ለብዙዎች ዕዉ
ራንም ያዩ ዘንድ ብርሃንን ሰጣቸው ።
ጌታ ኢየሱስም መልሶ እንዲህ አላቸው ፡ ሂዳችሁ ፳፪
ያያችሁትንና የሰማችሁትን ለዮሐንስ ንገሩት ፡ ዕዉ
ሮች ያያሉ ፡ አንካሶችም ይሄዳሉ ፡ ለምጻሞች ይነ
ፃሉ ፡ ደንቆሮችም ይሰማሉ ፡ ሙታን ይነሣሉ ፡ ድኾች
ወንጌልን ይማራሉ ፡ ደስ ይላቸዋል ። ኢሳ ፳፱ ፡
፲፰ ። ፴፭ ፡ ፭ ።
በእኔ የማይጠራጠሩ ንኡዳን ናቸው ። ፳፫

## ክፍል ፴፫ ፡ ዮሐንስ መጥምቅን ስለ ማመስገኑ ።

የዮሐንስ ደቀ መዛሙርት ከሄዱ በኋላ ለሕዝቡ ፳፬
ስለ ዮሐንስ መጥምቅ እንዲህ ይላቸው ጀመር ፡ ምን
ልታዩ ወደ ምድረ በዳ ወጣችሁ ? ከነፋስ የተነሣ
የሚወዛወዘውን ሸንበቆ ነውን ?
ወይስ ምን ልታዩ ወጣችሁ ፡ በቀጭን ልብስ ፳፭
ያጌጠውን ሰው ነውን ? በክብር ልብስ ያጌጡስ በነ
ገሥታት ቤት አሉ ።

፳፮ ወምንተኑመ ወፃእክሙ ትርአዩ ፡ ነቢየኑ ፡ እወ እብለ
ክሙ ፡ የዐቢ እምነቢይ ።
፳፯ ዝ ውእቱ ዘበእንቲአሁ ተጽሕፈ ፡ ናሁ አነ እፌኑ
መልአክየ ቅድመ ገጽከ ዘይጸይሕ ፍኖተከ በቅድ
ሜከ ።
፳፰ አማን እብለክሙ ኢተንሥአ እምውሉደ አንስት ዘየ
ዓቢ እምዮሐንስ መጥምቅ ወኢመኑሂ ፡ ወበመንግ
ሥተ እግዚአብሔርሰ ዘይንእስ የዓብዮ ።
፳፱ ወሰሚዖሙ ኵሉሙ ሕዝብ ወመጸብሐን አጽደቅዎ
ለእግዚአብሔር እስመ ተጠምቁ ጥምቀተ ዮሐንስ ።

፴ ወፈሪሳውያንሰ ወጸሐፍተ ሕግ በለዉ ትእዛዘ እግዚ
አብሔር እስመ ኢተጠምቁ በኀቤሁ ።

፴፩ በምንት አስተማስሎሙ ለሰብአ ዛቲ ትውልድ ፡ ወመነ
ይመስሉ ።
፴፪ ይመስሉ ደቂቀ እለ ይነብሩ ውስተ ምሥያጥ ወይጼ
ውዑ ቢጾሙ ወይብልዎሙ ኀለይነ ለክሙ ወኢዘፈን
ክሙ ፡ አስቆቀውነሂ ለክሙ ወኢበከይክሙ ።
፴፫ እስመ መጽአ ዮሐንስ መጥምቅ ኢይበልዕ እክለ
ወኢይሰቲ ወይነ ፡ ወትብልዎ ጋኔን ብቱ ።
፴፬ ወመጽአ ወልደ እጓለ እመሕያው ይበልዕ ወይሰቲ ፡
ወትቤሉ ነዋ ብእሲ በላዒ ወሰታዪ ወይን ዓርከ መጸ
ብሐን ወኃጥኣን ።
፴፭ ወጸድቀት ጥበብ እምኵሉ ውሉዳ ።

ክፍል ፴ወ፬ ፡ በእንተ ፈሪሳዊ ወኃጥእት ብእሲት ።

፴፮ ወይቤሎ አሐዱ እምፈሪሳውያን ከመ ይምሳሕ በኀ
ቤሁ ወበአ ቤተ ፈሪሳዊ ወረፈቀ ።

፳፯ ወመጽአት ብእሲት ኃጥእት እምሰብአ ይእቲ ሀገር
አእሚራ ከመ ይመስሕ ውስተ ቤተ ፈሪሳዊ ፡ ወተሣ
የጠት ዕፍረተ ዘአልባስጥሮስ ።
፴፰ ወቆመት ድኅሬሁ ኀበ እገሪሁ ወበከየት ወአርሐሰት
እገሪሁ በአንብዓ ወትመዘምዝ በሥእርተ ርእሳ ወት
ስዕም እገሪሁ ወትቀብእ ዕፍረተ ።
፴፱ ወርእዮ ፈሪሳዊ ዘጸውዖ ሐለየ በልቡ ወይቤ ፡ ሶበሁ
ነቢይ ውእቱ ዝንቱ እምኢያእመረኑ ከመ ኃጥእት
ይእቲ ዛቲ ብእሲት እንተ ትገሥሦ ።

፵ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ ስምዖን ብየ
ዘእብለከ ፡ ወይቤሎ ሊቅ በል ።
፵፩ ወይቤሎ ክልኤቱ ጼፈድይዎ ለአሐዱ በዓለ ዕዳ ፡
አሐዱ ይፈድዮ ኀምስተ ምእተ ዲናረ ፡ ወካልኡኒ
ኃምሳ ።
፵፪ ወኃጢአሙ ዘይፈድይዎ ኀደገ ሎሙ ለክልኤሆሙ ፡
መኑ እንከ ርቱዕ ፈድፋደ ያፈቅሮ እምኔሆሙ ።

ወይስ ምን ልታዩ ወጣችሁ ፡ ነቢይን ነው ? እው ፳፮
ነት እላችኋለሁ ከነቢይ ይበልጣል ። ዮሐ ፩ ፡ ፳፱ ።
"እነሆ መንገድህን የሚጠርግ መልእክተኛዬን በፊ ፳፯
ትህ እልካለሁ" ተብሎ ስለ እርሱ የተጻፈለት ይህ
ነው ።ሚል ፫ ፡ ፩ ። ማቴ ፲፩ ፡ ፪ ። ማር ፩ ፡ ፪ ።
እውነት እላችኋለሁ ከሴቶች ከተወለዱት ከዮሐንስ ፳፰
መጥምቅ የሚበልጥ ማንም አልተነሣም ፡ በመንግ
ሥተ ሰማያት ግን ፡ ታናሹ ይበልጠዋል ። ምዕ ፩ ፡ ፲፫ ።
ሕዝቡ ሁሉ ቀራጮችም በሰሙ ጊዜ እግዚአብሔርን ፳፱
አመኑበት ፡ የዮሐንስን ጥምቀት ተጠምቀው ነበርና ።
ማቴ ፳፩ ፡ ፴፪ ።
ፈሪሳውያንና የሕግ ጻፎች ግን የእግዚአብሔርን ፴
ትእዛዝ እምቢ አሉ ፡ ከእሱ አልተጠመቁምና ። የሐ
ሥራ ፲፫ ፡ ፵፯ ።
የዚችን ትውልድ ሰዎች በምን እመስላቸዋለሁ ? ፴፩
ማንንስ ይመስላሉ ?
በገበያ ተቀምጠው ባልንጀሮቻቸውን ጠርተው እቀኝ ፴፪
ቀንላችሁ አልዘፈናችሁም ፡ሙሾ አወጣንላችሁ
አላለቀሳችሁም የሚሏቸውን ልጆች ይመስላሉ ።
ዮሐንስ መጥምቅ መጣ ፡ እህል አይበላም ፡ ወይን ፴፫
አይጠጣም ፡ ጋኔን አለበት አላችሁት ።
የሰው ልጅ መጣ ፡ ይበላል ይጠጣል ፡ እናንተ ግን ፴፬
የሚበላ ፡ ወይን የሚጠጣ ፡ የኃጥአንና የቀራጮች
ወዳጅ ሰው እነሆ አላችሁት ።
ጥበብ ከልጆቿ ሁሉ ታመነች ። ፴፭

ክፍል ፴፬ ፡ ስለ ፈሪሳዊውና ስለ ኃጢአተኛዪቱ ሴት ።

ከፈሪሳውያንም አንዱ ከእሱ ዘንድ ምሳ እንዲበላ ፴፮
ምሳ ብላልኝ ብሎት ወደ ፈሪሳዊው ቤት ገብቶ
ለምሳ ተቀመጠ ። ምዕ ፲፩ ፡ ፴፯ ።
ከዚያች አገር ሰዎችም አንዲት ኃጢአተኛ ሴት በፈ ፴፯
ሪሳዊ ቤት ምሳ እንደሚበላ አውቃ ፡ የአልባስጥሮስ
ሽቱን ገዝታ መጣች ። ማቴ ፳፯ ፡ ፯ ።
በስተኋላው ከእግሩ አጠገብ ቆማ እያለቀሰች እግሮ ፴፰
ቹን በእንባዋ አራሰች ፡ እግሮቹንም ትስም በራስ
ጠጕሯ ታሸው ፡ ሽቱንም ትቀባው ነበር ። ዮሐ ፲፪ ፡ ፫ ።
የጠራው ፈሪሳዊም ባየ ጊዜ ፡ ይህ ነቢይማ ቢሆን ፴፱
ኖሮ የምትዳሥሠው ይህች ሴት ኃጢአተኛ እንደ
ሆነች ባላወቀም ነበርን ! ብሎ በልቡ አሰበ ። ምዕ
፲፭ ፡ ፪ ።
ጌታ ኢየሱስም መልሶ ስምዖን ! የምልህ ነገር አለኝ ፵
አለውና ፡ መምህር ! ተናገር አለው ።
እሱም እንዲህ አለው ፡ ለአንድ አበዳሪ ሁለት ተበዳ ፵፩
ሪዎች አሉት ፡ አንዱ አምስት መቶ ወቄት ይከፍለ
ዋል ፡ ሁለተኛውም አምሳ ወቄት ይከፍለዋል ።
የሚከፍሉትም ባጡ ጊዜ ለሁለቱም ተወላቸው ፡ ፵፪
እንግዲህ ከሁለቱ በጣም ሊወደው የሚገባው ማን
ኛው ነው ? ቆላ ፪ ፡ ፲፫ ።

፵፫ ወተሠጥወ ስምዖን ወይቤሎ ፡ እብልሰ ዘብዙኃ ኀደገ
ሎቱ ፡ ወይቤሎ ሠናየ ፈታሕከ ።
፵፬ ወተመይጠ ኀበ ይእቲ ብእሲት ፡ ወይቤሎ ለስምዖን
ትሬእያኑ ለዛቲ ብእሲት በእኩ ቤተከ ወኢ.ወሀብከኒ
ማየ ጥቀ ለእገርየ ወይእቲሰ በክየት ወበአንብዓ አር
ሐሰት እገርየ ወበሥእርታ መዝመዘተኒ ።

፵፭ ወአንተሰ ኢ.ተአማኅከኒ ወይእቲሰ እምዘበእኩ ኢ.ያ
ንተገት ስዒመ እገርየ ።
፵፮ ወአንተሰ ኢ.ቀባእከኒ በዘይት ርእስየ ወይእቲሰ ዕፍ
ረተ ቀብአተኒ ለእገርየ ።
፵፯ ወበእንተ ዝንቱ እብለከ ተኃድገ ላቲ ኃጢአታ ብዙኃ
እስመ ብዙኀ አፍቀረተኒ ወዘሰ ውኁደ አፍቀረኒ
ውኁድ ኃጢአቱ ይትኃደግ ሎቱ ፡ ወዘሰ ብዙኀ አፍ
ቀረኒ ብዙኀ ይትኃደግ ሎቱ ።
፵፰ ወይቤላ ለይእቲ ብእሲት ተኃድገ ለኪ ኃጢአትኪ ።

፵፱ ወአኀዙ እለ ይረፍቁ ይበሉ በበይናቲሆሙ ፡ መኑ
ውእቱ ዝንቱ ዘየኃድግ ኃጢአተ ።
፶ ወይቤላ ለይእቲ ብእሲት ፡ ሃይማኖትኪ አድኃነተኪ
እትዊ በሰላም ።

ስምዖንም መልሶ ብዙውን የተወለት ነው እላለሁ ፵፫
አለው ፡ ጌታም መልካም ፈረድክ አለው ።
ወደዚያች ሴት መለስ ብሎም ስምዖንን እንዲህ ፵፬
አለው ፡ ይህቺን ሴት ታያታለህን? ወደ ቤትህ ገባሁ ፡
ለእግሮቼም ውኃ ስንኳ ፈጽመህ አልሰጠኸኝም ፡
ይህች ግን አልቅሳ በእንባዋ እግሬን አጠበችኝ ፡
በራስ ጠጕሯም አሸችኝ ።[ዘፍ ፲፰ ፡ ፬ ። ዮሐ ፲፫ ፡ ፭ ።
አንተስ ሰላምታ አልሰጠኸኝም ፡ እሷ ግን ከገባሁ ፵፭
ጀምሮ እግሬን ከመሳም አላቋረጠችም ።
አንተ ራሴን በዘይት አልቀባኸኝም ፡ እሷ ግን ሽቱ ፵፮
ቀባችኝ ። ማቴ ፳፮ ፡ ፯ ።
ስለዚህም ብዙ ኃጢአቷ ተሠረየላት ፡ እጅግ ወዳኛ ፵፯
ለችና ፡ ጥቂት የሚወደኝ በጥቂቱ ይሠረይለታል ፡
ብዙ የሚወደኝም በብዙ ይሠረይለታል እልሃለሁ ።

ያችንም ሴት ኃጢአትሽ ተሠረየልሽ አላት ። ምዕ ፵፰
፭ ፡ ፳፩ ።
ተጋባገሮቹም እርስ በርሳቸው ኃጢአትን የሚያስተ ፵፱
ሠርይ ይህ ማነው? ይሉ ጀመር ።
ሴቲቱንም ሃይማኖትሽ አዳነችሽ፡ በሰላም ግቢ አላት ። ፶
ምዕ ፰ ፡ ፵፰ ። ማር ፭ ፡ ፴፬ ።

ምዕራፍ ፰ ፤

ክፍል ፴ወ፫ ፡ በእንተ ዑደቱ

አህጉረ ገሊላ ።

፩ ወእምዝ በሳኒታ አንሶሰወ እግዚእ ኢየሱስ ውስተ
አህጉር ወአዕፃዳት ወሰበከ ሎሙ ወመሀሮሙ በእ
ንተ መንግሥተ እግዚአብሔር ወምስሌሁ ዐሠርቱ
ወክልኤቱ አርዳኢሁ ።
፪ ወአንስትኒ እለ አሕየዎን እምአጋንንት እኩያን ወእ
ምደዌሆን ወእማንቱ ማርያም እንተ ይብልዋ መግ
ደላዊት እንተ ሰብዐቱ አጋንንት ወፅኡ እምኔሃ ።

፫ ወሐና ብእሲተ ኩዛ መጋቢሁ ለሄሮድስ ፡ ወሶስና ፤
ወካልኣትኒ ብዙኃት እለ ተልእክዎ በንዋዮን ።

ክፍል ፴ወ፬ በእንተ ምሳሌ ዘዘራኢ ።

፬ ወእንዘ ያጸምእዎ ኵሉ ሕዝብ ወእለኒ መጽኡ ኀቤሁ
እምኵሉ አህጉር ይቤሎሙ ምሳሌ እንተ ከመዝ ።

፭ ወፈረ ዘይዘርእ ከመ ይዝራእ ዘርአ ፡ ወእንዘ ይዘርእ
በ ዘወድቀ ውስተ ፍኖት ፡ ወመጽኡ ሰብእ ወኬድዎ
ወበልዕዎ አዕዋፈ ሰማይ ።
፮ ወበ ዘወድቀ ውስተ ኰኵሕ ፡ ወበቀኒሎ የብሰ በጊዜሃ
እስመ አልቦ ሥርው ።

ምዕራፍ ፰ ፤

ክፍል ፴፫ ፡ በገሊላ አውራጃዎች

ተዘዋውሮ ስለ ማስተማሩ ።

ከዚህም በኋላ በማግስቱ ጌታ ኢየሱስ በየሀገሩ በየ ፩
መንደሩ ተመላለሰ ፡ የእግዚአብሔርን መንግሥት
ሰበከላቸው አስተማራቸው ፡ ዐሥራ ሁለቱ ደቀ መዛ
ሙርቱም አብረዉት ነበሩ ። ምዕ ፬ ፡ ፵፫ ። ፯ ፡ ፲፫ ።
ከክፉ አጋንንትና ከልዩ ልዩ ደዌያቸው የፈወሳቸው ፪
ሴቶችም አብረዉት ነበሩ ፡ እነርሱም መግደላዊት
የሚሉዋት ሰበት አጋንንት የወጡላት ማርያም ።
ምዕ ፲፩ ፡ ፳፯ ።
የሄሮድስ አዛዥ የነበረው የኩዛ ሚስት ዮሐና ፡ ሶስና ፫
ናቸው ፡ ሌሎችም በገንዘባቸው ያገለገሉት ብዙዎች
ነበሩ ። ማር ፲፭ ፡ ፵ - ፵፩ ።

ክፍል ፴፬ ፡ ስለ ዘሪ ምሳሌ ።

ሕዝብ ሁሉ ፡ ከየሀገሩ ሁሉ ወደርሱ የመጡት ሲያ ፬
ዳምጡት እንዲህ ያለ ምሳሌ ነገራቸው ። ማቴ ፲፫ ፡
፩ - ፳፫ ። ማር ፬ ፡ ፩ - ፳፭ ።
ገበሬ ዘሩን ሊዘራ ወጣ ፡ ሲዘራም በመንገድ የወደቀ ፭
ዘር አለ ፡ ሰዎች መጥተው ረገጡት ፡ የሰማይ ወፎ
ችም በሉት ።
ከአለት ላይ የወደቀ ዘር አለ ፡ በቅሎም ወዲያው ፮
ደረቀ ፡ ሥር አልነበረውምና ።

| ፻፸ | ወንጌል ዘሉቃስ ፰ ። | የሉቃስ ወንጌል ፰ ። | |
|---|---|---|---|
| ፯ | ወበ ዘወድቀ ውስተ ሦክ ፡ ወበቍሉ ጠበቆ ሦክ ። | በእሾኽ መካከል የወደቀ ዘርም አለ ፡ ከበቀለም በኋላ እሾኽ አነቀው ። | ፯ |
| ፰ | ወበ ዘወድቀ ውስተ ምድር ሠናይት ፤ ወበቈለኒ ፤ ወፈረየኒ ምእተ ምክዕቢተ ፤ ወዘንተ ብሂሎ ይቤሎሙ ዘቦ ዕዝነ ሰሚዐ ለይስማዕ ። | በመልካም ምድር ላይም የወደቀ ዘር አለ ፡ በቀለ መቶ ዕጥፍም አፈራ ፡ ይህንም ብሎ ዠሮ ያለው መስማትን ይስማ አላቸው ። ዘፍ ፳፮ ፡ ፲፪ ። | ፰ |
| ፱ | ወተስእልዎ አርዳኢሁ ወይቤልዎ ምንትኑ ይእቲ ዛቲ ምሳሌ ። | ደቀ መዛሙርቱም ይህቺ ምሳሌ ምንድር ናት ? ብለው ጠየቁት ። | ፱ |
| ፲ | ወይቤሎሙ ለክሙ ተውህበ ታእምሩ ምሥጢራ ለመንግሥተ እግዚአብሔር ፡ ወለእልክቱሰ በምሳሌ ከመ ርእዮሙኒ ኢይርአዩ ወሰሚዖሙኒ ኢይስምዑ ፡ ወኢይለብዉ ። | እርሱም እንዲህ አላቸው ፡ የእግዚአብሔርን መንግሥት ልታውቁ ለእናንተ ተሰጥቷችኋል ፡ ለነዚያ ግን በምሳሌ ነው "አይተው እንዳያዩ ፡ ሰምተውም እንዳ ይሰሙ እንዳያስተውሉም" ። ኢሳ ፯ ፡ ፱ - ፲ ። | ፲ |
| ፲፩ | ወከመዝ ይእቲ ምሳሌሃ ፡ ዘርእሰ ቃለ እግዚአብሔር ውእቱ ። | ምሳሌዋም እንዲህ ነው ፡ ዘር የእግዚአብሔር ቃል ነው ። ፩ ጴጥ ፩ ፡ ፳፫ ። | ፲፩ |
| ፲፪ | ወዘሰ ውስተ ፍኖት ፡ እሉ እሙንቱ እለ ይሰምዑ ቃለ ፡ ወይመጽእ ሰይጣን ወይነሥእ ለቃል እምል በሙ ከመ ኢይእመኑ ወኢይሕየዉ ። | በመንገድ የተመሰሉ ፡ የሚሰሙ አምነውም እንዳ ይድኑ ሰይጣን መጥቶ ቃልን ከልባቸው የሚወስድ ባቸው ናቸው ። ማር ፬ ፡ ፲፫ ። | ፲፪ |
| ፲፫ | ወዘሰ ውስተ ኰኵሕ ፡ እለ ሰሚዖሙ ይትዌከፍዎ ለነገር በፍሥሓ ፡ ወበሕቱ ሥርው አልቦሙ ለሰበሃ ዳእሙ የአምኑ ፡ ወእምከመ ተመንደቡ የዐልዉ ። | በአለት የተመሰሉ ሰምተው ነገሩን በደስታ የሚቀ በሉት ናቸው ፡ ግን ለጊዜው ያምናሉ እንጂ መሠ ረት የላቸውምና ፡ መከራ ባገኛቸው ጊዜ ፈጥነው ይክዳሉ ። | ፲፫ |
| ፲፬ | ወዘሰ ውስተ ሦክ ፡ እሉ እሙንቱ እለ ይሰምዑ ቃለ ወሐሊና ብዕል ወትካዘ መንበርት ወሐውዘ ተድላ ወፈጊዕ ያጠውቆሙ ወኢይገብሩ ። | በእሾኽም መካከል ባለው መሬት የተመሰሉ እነ ዚህ ናቸው ፡ ቃልን የሚሰሙ ለሀብት ማሰብ ፡ ለኑሮ መቈርቈር የምቾት ማማርና መደሰት አስጨንቋቸው ያለ ፍሬ የሚያስቀራቸው ናቸው ። ፊል ፩ ፡ ፲፩ ። | ፲፬ |
| ፲፭ | ወዘሰ ውስተ ምድር ሠናይት ፡ እሉ እሙንቱ እለ ይሰ ምዑ ቃለ በሠናይ ልብ ወየዐቅብዎ ወበጥቡዕ ይት ዔገሡ ወያጠብዑ ወይፈርዩ ። | በመልካም ምድር የተመሰሉም እነዚህ ናቸው ፡ ቃልን በመልካም ልብ ሰምተው የሚጠብ ቁትና ጨክነው መከራውን ታግሠው የሚያፈሩ ናቸው ። ግብ ሐዋ ፲፯ ፡ ፲፬ ። ዕብ ፲ ፡ ፴፯ ። | ፲፭ |
| ፲፮ | ወአልቦ ዘየኀቱ ማኀቶተ ወይከድና ንዋየ ወያነብራ ታሕተ ዓራት ዘእንበለ ዲበ ተቅዋማ ከመ ይርአዩ ብርሃነ እለ ያንሶስዉ ። | መብራትን አብርቶ ዕቃ ከድኖ ከአልጋ በታች የሚያኖራት የለም ፡ የሚመላለሱት ብርሃኗን ያዩ ዘንድ በመቅረዝ ላይ ያኖራታል እንጂ ። ማር ፬ ፡ ፳፩ - ፳፭ ፤ ማቴ ፭ ፡ ፲፭ ። | ፲፮ |
| ፲፯ | ወአልቦ ኅቡእ ዘኢይትከሠት ፡ ወአልቦ ክዱን ዘኢያስተርኢ ወገሃደ ይከውን ። | የማይገለጥ የተሠወረ የለም ፡ የማይታይ የተከደነ የለም ፡ ግልጥ ይሆናል እንጂ ። ማቴ ፲ ፡ ፳፯ ። | ፲፯ |
| ፲፰ | ወአእምሩ እንከ ዘከመ ትሰምዑ ፡ እስመ ለዘቦ ይሁብዎ ፡ ወለዘሰ አልቦ ፡ እለሂ ቦ የኀይድዎ ። | እንግዲህ እንዴት እንደምትሰሙ አስተውሉ ፡ ላለው ይሰጡታልና ፡ የሌለውን ግን ያለውንም ይወስዱ በታልና ። ምዕ ፲፱ ፡ ፳፯ ። | ፲፰ |

## ክፍል ፴ወ፯ ፡ በእንተ አዝማዲሁ ።

## ክፍል ፴፯ ፡ ስለ ዘመዶቹ ።

| | | | |
|---|---|---|---|
| ፲፱ | ወመጽኡ ኀቤሁ እሙ ወአኀዊሁ ወስእኑ ረኪቦቶ እስመ ጽፉቅ ሰብእ ። | እናቱና ወንድሞቹ ወደርሱ መጡ ፡ ግን ሊያገኙት አልቻሉም ሰው እጅግ ብዙ ነበርና ። ማቴ ፲፪ ፡ ፵፯ - ፶ ። ማር ፫ ፡ ፴፩ - ፴፭ ። | ፲፱ |
| ፳ | ወይቤልዎ እምከ ወአኀዊከ አፍአ ይቀውሙ ወይፈ ቅዱ ይርአዩከ ። | እናትህና ወንድሞችህ ከውጭ ቆመዋል ፡ ሊያዩህም ይሻሉ አሉት ። | ፳ |
| ፳፩ | ወአውሥአ ወይቤሎሙ እምየ ወአኀውየ እሉ እሙ ንቱ እለ ይሰምዑ ቃለ እግዚአብሔር ወይገብሩ ። | እርሱም መልሶ እናቴና ወንድሞቼ የእግዚአብሔርን ቃል ሰምተው የሚሠሩ እሊህ ናቸው ፡ አላቸው ። | ፳፩ |

፳ ወሣልሱኒ ይቤሎ ብእሲተ አውሰብኩ ወበእንተዝ
ኢይክል መጺአ ።
፳፩ ወገብአ ገብሩ ወነገሮ ዘንተ ለእግዚኡ ወይእተ ጊዜ
ተምዐ በዐለ ቤት ወይቤሎ ለገብሩ ሑር ፍጡነ
ውስተ መራኅብት ወውስተ አስኳተ ሀገር ወአምጽእ
ሊተ ዝየ ነዳያነ፣ ወጽኑሳነ፣ ወምስኪናነ፣ ወዕዉ
ራነ፣ ወስቡራነ ።
፳፪ ወእምዝ ይቤሎ ገብሩ ገበርኩ እግዚኦ በከመ አዘዝ
ከኒ ወዓዲ ቦ መካን ።
፳፫ ወይቤሎ እግዚኡ ለገብሩ ሑር ፍጡነ ውስተ ፍናው
ወውስተ ጥቅመ ሀገር ወበግብር አብእ ሰብአ ከመ
ይምላእ ቤትየ ።
፳፬ እብለክሙ ከመ አሐዱሂ እምእልክቱ ሰብእ እለ
ጸዋዕኩ ኢይጥዕምዋ ለበዓልየ ።

ክፍል ፸ወ፮፣ በእንተ ተሊወተ እግዚእ ።

፳፭ ወእምዝ እንዘ የሐውሩ ምስሌሁ ብዙኃን ሰብእ
ተመይጠ ወይቤሎሙ ።
፳፮ ዘይመጽእ ኀቤየ ወይፈቅድ ይትልወኒ ለእመ ኢጸ
ልአ አባሁ ወእሞ ወብእሲቶ ወቤቶ ወውሉዶ ወአ
ኀዊሁ ወአኃቲሁ ወዓዲ ነፍሶሂ ኢይክል ከዊነ
ረድእየ ።
፳፯ ወዘኢይጸውር መስቀሎ ወኢይመጽእ ይትልወኒ
ኢይክል ከዊነ ረድእየ ።

ክፍል ፸ወ፯፣ ምሳሌ በእንተ ዘየሐንጽ ማኅፈደ ።

፳፰ ወእመቦ አሐዱ እምኔክሙ ዘይፈቅድ ይሕንጽ ማኅ
ፈደ አኮኑ ይቀድም ወይነብር ወየሐስብ ፃእፃአ
እመቦ ዘየአክሎ ከመ ይሣርር መሠረቶ ።
፳፱ ከመ ሣሪሮ መሠረተ ለእመ ስእነ ፈጽሞ ኵሎሙ
እለ ርእይዎ ይእኀዙ ይሣለቁ ላዕሌሁ ።
፴ እንዘ ይብሉ ዝንቱ ብእሲ አኀዘ ይሕንጽ ወስእነ
ፈጽሞ ።
፴፩ ወእመኒ ፈቀደ ንጉሥ ይሑር ይጽብአ ለካልእ
ንጉሥ አኮኑ ይቀድም ወይነብር ወይመክር ለእመ
ይክል በእልፍ ፀቢኦቶ ለዘይመጽእ ኀቤሁ ምስለ
ክልኤ እልፍ ።
፴፪ ወእመ አኮሰ እንዘ ርኁቅ ውእቱ ይፌኑ ሐዋርያተ
ትንብልና ኀቤሁ ወይዜንውዎ ሰላመ ።
፴፫ ወከመዝ እንከ ኵሉ ዘእምኔክሙ ዘኢወፅአ እም
ኵሉ ወዘኢይትናከር ኵሎ ዘዚአሁ ንዋየ ኢይክል
ከዊነ ረድእየ ።
፴፬ ሠናይ ውእቱ ፄው ወእመሰ ፄው ለስሐ በምንት
እንከ ይቄስምዎ ።
፴፭ አኮኑ ይገድፍዎ አፍአ ውስተ መሬት፣ ዘቦ ዕዝነ
ሰሚዐ ለይስማዕ ።



ሦስተኛውም ሚስት አግብቻለሁ ስለዚህ ልመጣ ፳
አልቻልኩም አለው፣ ፩ ቆሮ. ፯ ፴፫ ።
አገልጋዩም ተመልሶ ለጌታው ይኸንኑ ነገረው፣ ያን ፳፩
ጊዜም ባለቤቱ ተቈጣና አገልጋዩን ፈጥነህ ወደ አደ
ባባይና ወደ አገሩ ሜዳ ሂደህ ድኾችን ችግረኞችን
ጦም-አዳሮችን ፣ ዕውሮችንና አንካሶችን ወደዚህ
አምጣልኝ አለው ።
ከዚህም በኋላ አገልጋዩ አቤቱ! እንደ አዘዝከኝ አደ ፳፪
ረግኹ፣ አሁንም ቦታ አለ አለው ።
ጌታውም አገልጋዩን ወደ መንገዶች ወደ አገሩ መግ ፳፫
ቢያ በር ሂድና ቤቴ እንዲመላ በግድ ሰውን ሰብስበህ
አግባ አለው፣ ዘፍጥ. ፲፱ ፫ ።
ከእነዚህ ከጠራኋቸው አንድ ስንኳ ግብዣዬን እንደ ፳፬
ማይቀምሷት እነግራችኋለሁ፣ ማቴ. ፳፩ ፵፫ ።

ክፍል ፸፮፣ ጌታን ስለ መከተል ።

ከዚህም በኋላ ብዙ ሰዎች አብረዉት ሲሄዱ መለስ ፳፭
ብሎ እንዲህ አላቸው ምዕ. ፲፰ ፳፱-፴፣ ፲ ፴፯-፴፰ ።
ወደኔ የሚመጣ ሊከተለኝም የሚወድ አባቱንና እና ፳፮
ቱን ፣ ሚስቱን ፣ ቤቱንና ልጆቹን፣ ወንድሞቹንና
እኅቶቹን ካልጠላ ደግሞም ሰውነቱን ካልጠላ ደቀ
መዝሙሬ ሊሆን አይችልም፣ ዘዳግ ፲፫ ፯፣ ፴፫ ፱ ።
መስቀሉን ተሸክሞ ሊከተለኝ የማይመጣ ደቀ መዝ ፳፯
ሙሬ ሊሆን አይችልም፣ ምዕ. ፱ ፳፫፣ ማር ፰ ፴፬ ።

ክፍል ፸፯ ፣ ቤት ስለሚሠራ ምሳሌ ።

ከእናንተ ግንብ ሊሠራ የሚወድ አንድ ሰው ቢኖር ፳፰
የሚበቃ ገንዘብ ቢኖረው መሠረቱን ይጥል ዘንድ
አስቀድሞ ተቀምጦ ጣጣውን ያስብ የለምን? ።
መሠረት ጥሎ መጨረስ ያቃተው እንደሆነ ያዩት ፳፱
ሁሉ ሊዘብቱበት ይጀምራሉ ።
ይህ ሰው ሊሠራ ጀመረ ግን መጨረስ ተሳነው ፴
ብለው ።
ንጉሥ ሌላውን ንጉሥ ይወጋው ዘንድ ሊሄድ ቢወድ ፴፩
ሁለት እልፍ ይዞ ወደርሱ የሚመጣውን በአንድ
እልፍ ሊዋጋው ይችል እንደሆነ አስቀድሞ ተቀ
ምጦ ይመክር የለምን? ።
ያለዚያ ግን ገና ከሩቅ ሳለ የምልጃ መልክተኞችን ፴፪
ወደርሱ ይልካል እንታረቅ ብሏል ይሉታል፣ ኢሳ.
፶፭ ፳፬ ።
እንደዚህም ከእናንተ ወገን የሆነ ሁሉ፣ ከሁሉ ያል ፴፫
ወጣ የእርሱ ገንዘብ ከሆነው ሁሉ ያልተለየ ደቀ
መዝሙሬ ሊሆን አይችልም፣ ማቴ ፲፫ ፵፬ ።
ጨው መልካም ነው፣ ነገር ግን ጨው አልጫ ከሆነ ፴፬
እንግዲህ በምን ያጣፍጡታል? ማቴ. ፭ ፲፫፣ ማር. ፱ ፶፤
ወደ ውጭ አውጥተው ከመሬት ጋር ይጨምሩት የለ ፴፭
ምን? ፣"ዦሮ ያለው መስማትን ይስማ" ፤ ምዕ. ፰ ፰ ።

ምዕራፍ ፲ወ፭ ፤

ክፍል ፹ወ፯ ፡ በእንተ ምሳሌ ዘምእት አባግዕ ።

፩ ወቀርቡ ኀቤሁ መጸብሐን ወኃጥአን ይስምዕዎ ።

፪ ወአንጐርጐሩ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን እንዘ ይብሉ ዝንቱሰ ኃጥአነ ይትዌከፍ ወይበልዕ ምስሌሆሙ ።

፫ ወመሰለ ሎሙ ከመዝ ወይቤሎሙ ።

፬ እመቦ ብእሲ እምኔክሙ ዘቦ ምእት አባግዕ ወለእመ ተገድፈቶ አሐቲ እምኔሆን አኮኑ የኀድግ ተስዐ ወተስዐተ ውስተ ገዳም ወየሐውር ኀበ ተገድፈቶ እስከ ይረክባ ።

፭ ወእምከመ ረከባ ይፀውራ ዲበ መትከፍቱ እንዘ ይትፌሣሕ ።

፮ ወአቲዎ ቤቶ ይጼውዕ አዕርክቲሁ ወጐሮ ወይብሎሙ ተፈሥሑ ሊተ እስመ ረከብኩ በግዕትየ እንተ ተገድፈተኒ ።

፯ እብለክሙ ከመ ከመዝ ይከውን ዐቢይ ትፍሥሕት በሰማያት በበይነ አሐዱ ኃጥእ ዘይኔስሕ ፈድፋደ እምነ ተስዐ ወተስዐቱ ጻድቃን እለ ኢይፈቅዱ ይነስሑ ።

ክፍል ፹ወ፰ ፡ በእንተ ተረክቦተ ገመስ ።

፰ ወእመኒ ብእሲት ዘባቲ ዓሥሩ ጠፋልሐ አግሙስ ወለእመ ተገድፈታ አሐቲ እምኔሆን አኮኑ ታኀቱ ማኅቶተ ወትፈነቅል ኵሎ ዘውስተ ቤታ ወተኃሥሥ አስተሐሚማ እስከ ትረክብ ።

፱ ወእምከመ ረከበታ ትጼውዕ አዕርክቲሃ ወኀራ ወትብሎን ተፈሥሓ ሊተ እስመ ረከብኩ ገመስየ እንተ ተገድፈተኒ ።

፲ እብለክሙ ከመ ከማሁ ይከውን ፍሥሓ በሰማያት በቅድመ መላእክተ እግዚአብሔር በእንተ አሐዱ ኃጥእ ዘይኔስሕ ።

ክፍል ፹፱ ፡ በእንተ ወልድ ዘተኃጕለ ወተረክበ ።

፲፩ ወከዐበ ይቤሎሙ አሐዱ ብእሲ ቦቱ ክልኤቱ ደቂቅ ።

፲፪ ወይቤሎ ዘይንእስ ለአቡሁ አባ ሀበኒ መክፈልተ ርስትየ ዘይረክበኒ እምንዋይከ ፡ ወከፈሎ ንዋዮ ።

፲፫ ወእምድኅረ ኅዳጥ መዋዕል አስተጋብአ ኵሎ ዝኩ ወልዱ ዘይንእስ ወሖረ ወነገደ ርኁቀ ብሔረ ወበህየ ዘረወ ወአማሰነ ኵሎ ንዋዮ እንዘ የሐዩ በምርዓት ።

፲፬ ወአኅለቀ ኵሎ ንዋዮ መጽአ ረኃብ ዐቢይ ውስተ ውእቱ ብሔር ወተጸነሰ ።

፲፭ ወሖረ ወተጸምደ ኀበ አሐዱ እምሰብአ ውእቱ ብሔር ወፈነዎ ውስተ አዕፃዳ ወፍሩ ይርአይ አሕርወ።

፲፮ ወፈተወ ይጽገብ እምሐመረ ጽራዕ ዘይሴሰዩ አሕርው ወአልቦ ዘይሁቦ ።

ምዕራፍ ፲፭ ።

ክፍል ፹፯ ፡ ስለ መቶ በጎች ምሳሌ ።

ኃጢአተኞችና ቀራጮች ሊሰሙት ወደርሱ ቀረቡ ፡ ፩
ምዕ. ፭ ፳፱-፴ ።

ጻፎችና ፈሪሳውያንም ይህስ ኃጢአተኞችን ይወዳል ፪
አብሯቸውም ይበላል ብለው አንጐራጐሩ ።

እንዲህ ብሎም መሰለላቸው ። ፫

ከእናንተ መካከል መቶ በግ ያለው ሰው ቢኖር ከእ ፬
ነርሱ አንዲቱ ብትጠፋው ዘጠና ዘጠኙን በምድረ በዳ
ትቶ እስኪያገኛት ድረስ ወደ ጠፋችው ይሄድ የለ
ምን ? ፡ ሕዝ. ፴፬ ፲፩-፲፮ ።

ባገኛት ጊዜም ደስ እያለው በትከሻው ላይ ይሸከማ ፭
ታል ፡ ኢሳ. ፵ ፲፩ ።

ወደ ቤቱም በገባ ጊዜ ወዳጆቹን ጐረቤቶቹን ጠርቶ ፮
የጠፋችኝን በጌን አግኝቻለሁና ከኔ ጋር ደስ ይበላ
ችሁ ይላቸዋል ፡ ፩ ጴጥ. ፪ ፳፭ ።

እንዲሁ ንስሐ ከማይሹ ከዘጠና ዘጠኙ ጻድቃን ይልቅ ፯
ንስሐ ስለሚገባ ስለ አንድ ኃጢአተኛ በሰማይ ፍጹም
ደስታ እንደሚሆን እነግራችኋለሁ ፡ ምዕ. ፭ ፴፪ ።

ክፍል ፹፰ ፡ ስለ ጠፋችው ቀለበት መገኘት ።

ዐሥር ድሪም ያላት ሴት ብትኖር ከዐሥሩ አንዲቱ ፰
ብትጠፋት መብራት አብርታ በቤቷ ያለውን ሁሉ
እየፈነቀለች እስክታገኛት ድረስ ተግታ ትፈልግ የለ
ምን ? ።

ያገኘቻት እንደሆነም ወዳጆቿን ጎረቤቶቿን ጠርታ ፱
የጠፋችኝን ድሪሜን አግቻለሁና ከኔ ጋር ደስ ይበ
ላችሁ ትላቸዋለች ።

እንደዚሁም ንስሐ ስለሚገባ ስለ አንድ ኃጢአተኛ ፲
በእግዚአብሔር መላእክት ፊት በሰማያት ደስታ እን
ደሚሆን እነግራችኋለሁ ኤፌ. ፫ ፲ ።

ክፍል ፹፱ ፡ ጠፍቶ ስለ ተገኘው ልጅ ።

ዳግመኛም እንዲህ አላቸው ፡ አንድ ሰው ሁለት ፲፩
ልጆች ነበሩት ።

ታናሹ ልጁም አባቱን ፡ አባቴ ! ከገንዘብህ የሚደርሰ ፲፪
ኝን ክፍለህ ስጠኝ አለው ገንዘቡንም ከፍሎ ሰጠው ።

ከጥቂት ቀኖች በኋላም ያ ትንሹ ልጁ ሁሉም ሰብ ፲፫
ስቦ ወደ ሩቅ አገር ሄዶ በድርዓት እየኖረ በዚያ ገን
ዘቡን ሁሉ በትኖ ጨረሰ ፡ ምሳ. ፳፱ ፫ ።

ገንዘቡንም ሁሉ በጨረሰ ጊዜ በዚያ አገር ጽኑ ረኃብ ፲፬
መጣ እሱም ደኸየ ።

ሄዶም ከዚያ አገር ሰዎች ለአንዱ ተቀጠረ ሰውዬ ፲፭
ውም አሳማዎችን ይጠብቅ ዘንድ ወደርሻው ቦታ
ሰደደው ።

አሳማዎች ከሚበሉትም ተራንቃሞ ሊበላ ተመኘ ፲፮
ግን የሚሰጠው አልነበረም ።

፲፯ ወሐለየ በልቡ ወይቤ ሚ መጠን አግብርቲሁ ወገባ
እቱ ለአቡየ እለ ያተርፍዎ ለእክል ወአንሰ እመ
ውት በረኃብ በዝየ ።
፲፰ እትነሣእ ወአሐውር ኀበ አቡየ ወእብሎ አባ አበ
ስኩ በሰማይኒ ወበቅድሜከኒ ።
፲፱ ወኢይደልወኒ እንከ እሰመይ ወልደከ አላ ረስየኒ
ከመ አሐዱ እምአግብርቲከ ።
፳ ወተንሥአ ወሐረ ኀበ አቡሁ ወርእዮ አቡሁ እም
ርኁቅ ምሕሮ ወሮጸ ወሐቀፎ ክሣዶ ወሰዓሞ ።
፳፩ ወይቤሎ ወልዱ አባ አበስኩ በሰማይኒ ወበቅድሜ
ከኒ ኢይደልወኒ እንከ እሰመይ ወልደከ አላ ረስየኒ
ከመ አሐዱ እምአግብርቲከ ።
፳፪ ወይቤሎሙ አቡሁ ለአግብርቲሁ አምጽኡ ፍጡነ
አልባሰ ቅድዋተ ወአልብስዎ ወደዩ ኅልቀተ ውስተ
አፃብኢሁ ወአሣእነ ውስተ እገሪሁ ።
፳፫ ወአምጽኡ ላሕመ መግዝአ ወጥብሑ ንብላዕ ወን
ትፈሣሕ ።
፳፬ እስመ ዝንቱ ወልድየ ሞተኒ ወሐይወ ተኃጕለኒ
ወተረክበ ፡ ወአኀዙ ይትፈሥሑ ።
፳፭ ወወልዱሰ ዘይልኅቅ ሀለወ ውስተ ሐቅል ወሶበ
በጽሐ ኀበ ጽንፈ ሀገር ሰምዐ ዕንዚራ ወማኅሌተ ።
፳፮ ወጸውዐ አሐደ እምአግብርተ አቡሁ ወይቤሎ ምን
ትኑ ዝንቱ ዘእሰምዕ ።
፳፯ ወይቤሎ እስመ አተወ እኁከ ፡ ወጠብሐ አቡከ
ላሕመ መግዝአ እስመ ረከቦ ሕያዎ ።
፳፰ ወተምዐ ወአበየ በዊአ ወወፅአ አቡሁ ወአስተብቍዖ።
፳፱ ወአውሥአ ወይቤሎ ለአቡሁ ናሁ መጠነዝ ዓመተ
ተቀነይኩ ለከ ወግሙራ ኢኃለፍኩ እምትእዛዝከ
ወሊተሰ ኢወሀብከኒ ማሕስአ ጠሊ ጥቀ በዘእትፌ
ሣሕ ቦቱ ምስለ አዕርክትየ ወቢጽየ ።
፴ ወአቲዎሰ ዝንቱ ወልድከ ዘአኅለቀ ወበልዐ ኵሎ
ንዋየከ ምስለ ዘማት ጠባሕከ ሎቱ ላሕመ መግዝአ።
፴፩ ወይቤሎ አቡሁ ወልድየ አንተሰ ዘልፈ ሀለውከ
ምስሌየ ወኵሉ ዘዚአየ ዚአከ ውእቱ ።
፴፪ ወበሕቱ ርቱዕሰ ንትፈሣሕ እስመ ዝንቱ እኁከ
ሞተኒ ወሐይወ ፡ ተኀጕለኒ ወተረክበ ።

የሉቃስ ወንጌል ፲፭ ።

በልቡም እንዲህ ብሎ አሰበ እህል የተረፋቸው ፲፯
የአባቴ ሞያተኞችና አገልጋዮች ምን ያህል ናቸው !
እኔ ግን ከዚህ በረኃብ ልሞት ነው ፡ ኢሳ. ፵፯ ፰ ።
ተነሥቼ ወደ አባቴ ቤት እሄድና ፡ አባቴ እግዚአብ ፲፰
ሔርንም አንተንም በድያለሁ እለዋለሁ ኤር. ፫ ፲፪ ፡
መዝ. ፶፩ ፯ ።
እንግዲህ ልጅህ ልባል አይገባኝም ከአገልጋዮችህ ፲፱
እንደ አንዱ አድርገኝ እንጂ ።
ተነሥቶም ወደ አባቱ ሄደ አባቱም ከሩቅ አይቶት ፳
ራራለት ሮጦም አንገቱንም አቅፎ ሳመው ፡ መዝ. ፻፲
፲፫ ፡ ያዕ. ፬ ፰ ።
ልጁም አባቴ አንተንም እግዚአብሔርንም በድያለሁ ፳፩
ከእንግዲህ ወዲህ ልጅህ ልባል አይገባኝም ከአገል
ጋዮችህ እንደ አንዱ አድርገኝ እንጂ አለው ።
አባቱም አገልጋዮቹን ጠርቶ ያማሩ ያማሩ ልብሶችን ፳፪
ቶሎ አምጡና አልብሱት ፤ ለጣቱም ቀለበት አድር
ጉለት ፤ ለእግሩም ጫማ አጫሙት አላቸው ።
ኢሳ. ፷፩ ፲ ፡ ራእ. ዮሐ. ፫ ፲፰ ።
የሰባ ፍሪዳም አምጥታችሁ እረዱና እንብላ ደስ ፳፫
ይበለን ።
ይህ ልጄ ሞቶ ተነሥቷልና ጠፍቶም ተገኝቷልና ፡ ፳፬
ደስም ይላቸው ጀመር ፡ ኤፌ. ፪ ፩ ፡ ፭ ፲፬ ።
ታላቅ ልጁም በበረኻ ነበረና ተመልሶ ከመንደሩ ፳፭
አቅራቢያ በደረሰ ጊዜ የጨዋታውንና የመሰንቆውን
ድምፅ ሰማ ።
ከአባቱ አገልጋዮችም አንዱን ጠርቶ ይህ የምሰ ፳፮
ማው ምንድን ነው ? አለው ።
እርሱም ፡ ወንድምህ ከሄደበት መጥቶአልና አባትህ ፳፯
በሕይወት ስለ አገኘው የሰባ ፍሪዳን ስለ አረደ ነው
አለው ።
ተቈጥቶ አልገባም እንቢ አለ ፡ አባቱም ወጥቶ ማለ ፳፰
ደው ።
መልሶም አባቱን እንዲህ አለው ፡ እነሆ ይህን ፳፱
ያህል ዘመን ተገዝሁልህ ፈጽሞ ከትእዛዝህ አልወጣ
ሁም ፡ ለእኔ ግን ከባልንጀሮቼና ከወዳጆቼ ጋር ደስ
የምሰኝበት የፍየል ጠቦት ስንኳን አልሰጠኸኝም ።
ገንዘብህን ሁሉ ከአመንዝሮች ጋር በልቶ የጨረሰ ፴
ይህ ልጅህ በተመለሰ ጊዜ ግን የሰባ ፍሪዳን አረድ
ክለት ፡ ምሳ. ፳፱ ፫ ።
አባቱም እንዲህ አለው ፡ ልጄ አንተማ ዘወትር ከእኔ ፴፩
ጋር ነህ ፡ የእኔ የሆነ ሁሉ ያንተ ነው ።
ነገር ግን ይህ ወንድምህ ሞቶ ተነሥቷል ፡ ጠፍቶ ፴፪
ተገኝቷልና ደስ ልንሰኝ ይገባናል ፡ ቈላ. ፪ ፫ ።

### ምዕራፍ ፲ወ፮ ፡

### ክፍል ፹ወ፩ ፡ በእንተ መጋቤ ዓመፃ ።

፩ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ለአርዳኢሁ አሐዱ
ብእሲ ባዕል ቦቱ መጋቢ ወአስተዋደይዎ ኀቤሁ
ከመ ዘይዘሩ ኵሎ ንዋዮ ።

፪ ወጸውዖ እግዚኡ ወይቤሎ ምንትኑ ዝ ዘእሰምዕ
በእንቲአከ አግብእ እንከሰ ሐሳበ ምግብናከ እስመ
ኢትክውነኒ እንከ መጋቤ ሊተ ።

፫ ወሐለየ ውእቱ መጋቢ ወይቤ ምንተ እሬሲ ናሁ
ይስዕረኒ እግዚእየ እምግብናየ ሐሪሰኒ ኢይክል
ወስኢለኒ አኃፍር ።

፬ አአምር እንከሰ ዘእገብር እምከመ ሰዐረኒ እግዚእየ
እምግብናየ ከመ ይትወከፉኒ ውስተ አብያቲሆሙ ።

፭ ወጸውዖሙ ለአለ ይፈድይዎ ዕዳ ለእግዚኡ ወይቤሎ
ለቀዳማዊ ሚመጠን ዕዳ ዘትፈድዮ ለእግዚእየ ፡ ወይ
ቤሎ ምእት በመሥፈርተ ባዶስ ቅብእ ።

፮ ወይቤሎ ናሁኬ መጽሐፍከ ንበር ወጸሐፍ ፍጡነ
ኃምሳ ላዕሌከ ።

፯ ወይቤሎ ለካልኡኒ አንተሰ ሚመጠነ ትፈድዮ ለእግ
ዚእየ ፡ ወይቤሎ ምእት በመስፈርተ ቆሮስ ሥርናየ
ወይቤሎ ናሁኬ መጽሐፍከ ንበር ወጸሐፍ ፍጡነ
ሰማንያ ላዕሌከ ።

፰ ወንእዶ እግዚአብሔር ለመጋቤ ዐመፃ እስመ ከመ
ጠቢብ ገብረ እስመ ውሉደ ዝ ዓለም ይጠብቡ እም
ውሉደ ብርሃን በዓለሞሙ ።

፱ ወአነኒ እብለክሙ ግበሩ ለክሙ አዕርክተ እምንዋየ
ዓመፃ ከመ አመ የኃልቅ ንዋይክሙ ይትወከፉክሙ
እሙንቱሂ ውስተ አብያቲሆሙ ዘለዓለም ።

፲ ወዘሰ በውኁድ ምእመን በብዙኅኒ ምእመን ውእቱ ፡
ወዘሰ በኅዳጥ ዐማፂ በብዙኅኒ ዐማፂ ውእቱ ።

፲፩ ወሶበ በንዋየ ዓመፃ ሃይማኖት አልብክሙ በንዋየ
ጽድቅ መኑ የአምነክሙ ።

፲፪ ወሶበ በንዋየ ባዕድ ሃይማኖት አልብክሙ ዘዚአሁ
መኑ እንከ ይሁበክሙ ።

፲፫ አልቦ ገብር ዘይክል ተቀንዮ ለክልኤቱ አጋእዝት
ወእመ አኮ አሐደ ያፈቅር ወካልአ ይጸልእ ፡ ወእመ
አኮ ለአሐዱ ይትኤዘዝ ወለካልኡ የአቢ ፡ ኢትክ
ሉኬ ለእግዚአብሔር ተቀንዮ እንዘ ንዋየ ታፈቅሩ ።



### ምዕራፍ ፲፮ ፡

### ክፍል ፹፩ ፡ ስለ ዓመፀኛው መጋቢ ።

ጌታ ኢየሱስ ለደቀ መዛሙርቱ እንዲህ አላቸው ፩
አንድ ባለ ጸጋ ሰው መጋቢ ነበረው ገንዘቡን ሁሉ
የሚበትን ሰው እንደ መሆኑ ከእርሱ ዘንድ ከሰሱት ፡
ምዕ ፲፭ ፡ ፲፫ ።

ጌታውም ጠርቶ ስላንተ የምሰማው ይህ ምንድር ፪
ነው ? እንግዲህ ወዲህ ለእኔ መጋቢ አትሆነኝምና
የተሾምክበትን ሒሳብ አግባልኝ አለው ። መክ
፲፩ ፡ ፱ - ፲ ።

ያም መጋቢ አስቦ እንዲህ አለ ፡ ምን ላድርግ ! አሁን ፫
ጌታዬ ከሹመቴ ይሽረኛል ማረስ አልችልም መለ
መንም አፍራለሁ ።

እንግዲያስ ጌታዬ ከሹመቴ የሻረኝ እንደሆነ በቤ ፬
ታቸው ይቀበሉኝ ዘንድ የማደርገውን አውቃለሁ ።

ለጌታው ዕዳ የሚከፍሉትን ጠርቶ የመጀመሪያውን ፭
ለጌታዬ የምትከፍለው ዕዳ ምን ያህል ነው ? አለው ፡
መቶ ማድጋ ዘይት ነው አለው ።

እነሆ የጻፍክበት ደኅው ቁጭ በልና በአንተ ፮
ላይ ኃምሳ ማድጋ ብለህ ቶሎ ጻፍ አለው ።

ሁለተኛውንም አንተሳ ለጌታዬ ምን ያህል ትከፍለ ፯
ዋለህ ? መቶ ማድጋ ሥንዴ ነው አለው ፡ እነሆ ደብ
ዳቤህ ይኸው ቁጭ በልና በአንተ ላይ ሰማንያ
ብለህ ቶሎ ጻፍ አለው ።

እግዚአብሔርም ዐመፀኛውን መጋቢ አመሰገነው ፡ ፰
እንደ ብልህ ሰው ሠርቷልና ከብርሃን ልጆች ይልቅ
የዚህ ዓለም ልጆች በዓለማቸው ይራቀቃሉና ።
ዮሐ ፲፪ ፡ ፴፮ ፡ ኤፌ ፭ ፡ ፱ ፡ ፩ ተሰ ፭ ፡ ፭ ።

እኔም በኃላፊው ገንዘብ ለእናንተ ወዳጆችን አድ ፱
ርጉ ገንዘባችሁ ባለቀ ጊዜ እነርሱም በዘላለም ቤቶ
ቻቸው ይቀበሏችሁ ዘንድ ። ኢሳ ፴፪ ፲፯ - ፲፰ ፡ ዳን
፬ ፡ ፳፯ ፡ ማቴ ፮ ፡ ፳ - ፳፬ ። ፲ ፡ ፵ ፡ ፲፱ ፡ ፳፩ ።

በጥቂት የሚታመን በብዙ የታመነ ነው ፡ በጥቂት ፲
ያመፀም በብዙም ቢሆን ዐመፀኛ ነው ፡ ምዕ ፲፱ ፲፯ ፡
ማቴ ፳፭ ፳፩ ።

በኃላፊው ገንዘብ ታማኝነት ከሌላችሁ በማያልፈ ፲፩
ውማ ማን ያምናችኋል ?

በሌላው ገንዘብ ታማኝነት ከሌላችሁስ የራሱን ማን ፲፪
ይሰጣችኋል ? ።

ለሁለት ጌቶች መገዛትን የሚችል አገልጋይ የለም ፲፫
ካልሆነም አንዱን ይወዳል ፡ አንዱን ይጠላል ፡ ወይም
ለአንዱ ይታዘዛል ለአንዱ እንቢ ይላል ፡ እንዲሁም
ገንዘብን እየወደዳችሁ ለእግዚአብሔር መገዛትን
አትችሉም ፡ ማቴ ፮ ፳፬ ።

### ክፍል ፹ወ፪ ፡ በእንተ ተቃጽቦተ ፈሪሳውያን ።

፲፬ ወሰሚዖሙ ዘንተ ኵሎሙ ፈሪሳውያን ተቃጸብዎ
እስመ መፍቀርያነ ንዋይ እሙንቱ ።

፲፭ ወይቤሎሙ አንትሙሰ ትጼደቁ ለዓይነ ሰብእ ወእ
ግዚአብሔር የአምር ልበክሙ እስመ ዘበኀበ ሰብእ
ዓቢይ በኀበ እግዚአብሔር ትሑት ወምኑን ውእቱ ።

፲፮ ኦሪትኒ ወነቢያትኒ እስከ ዮሐንስ እምትክት ሰበኩ
በእንተ መንግሥተ እግዚአብሔር ወኵሉ ይትገፋዕ
በእንቲአሃ ።

፲፯ ወበሕቱ ይቀልል ሰማይ ወምድር ይኀልፍ እምትደቅ
አሐቲ ቃል እምኦሪት እምነቢያት ።

፲፰ ወኵሉ ዘይድኅር ብእሲቶ ወያወስብ ካልእተ ዘመወ
ወዘኒ ያወስብ ኅድግተ ዘማዊ ውእቱ ፡ ወእንተኒ
ደኃራ ምታ ለእመ ቀርበት ካልአ ዘመወት ።

### ክፍል ፹ወ፫ በእንተ ፩ዱ ባዕል ወአልአዛር ።

፲፱ ወሀሎ አሐዱ ብእሲ ባዕል ወይለብስ ሜላተ ወልብሰ
ቢሶስ ወቀጠንተ አልባስ ወይትፌጋዕ ኵሎ አሚረ ።

፳ ወሀሎ አሐዱ ነዳይ ዘስሙ አልአዛር ግዱፍ ውስተ
ዴዴሁ ለባዕል እንዘ ይደዊ በሕማመ ቍስል ።

፳፩ ወይፈቱ ይጽገብ እምፍርፋራት ዘይወድቅ እማእዱ
ለባዕል ወከለባትኒ ይመጽኡ ወይልሕሱ ቍሰሊሁ ።

፳፪ ወእምዝ ሞተ ዝኩ ነዳይ ወወሰድዎ መላእክት
ውስተ ሕፅነ አብርሃም ።

፳፫ ወሞተ ባዕልኒ ወተቀብረ ወበሲኦል አንሥአ አዕይ
ንቲሁ እንዘ ሀሎ ውስተ ደይን ፡ ወርእዮ ለአብርሃም
እምርኁቅ ወአልአዛርሃ ውስተ ሕፅኑ ።

፳፬ ወጸውዐ ወይቤ አባ አብርሃም ተሠሃለኒ ወፈንዎ
ለአልአዛር ከመ ይጥማዕ ጽንፈ አጽባዕቱ ማየ ወያ
ቍርረኒ ልሳንየ እስመ ሐመምኩ ፈድፋደ በዛቲ
እሳት ።

፳፭ ወይቤሎ አብርሃም ተዘከር ወልድየ ዘከመ ፈጋዕከ
ወተፈሣሕከ በሕይወትከ ወአልአዛርሰ ከማሁ ከመ
በተጽናስ ወይእዜሰ ከማሁ ከመ ውእቱ ይትፌሣሕ
በዝየ ወአንተሰ ተሐምም ።

፳፮ ወምስለ ዝንቱ ኵሉ ጸድፍ ዐቢይ ይከልአነ ማእከ
ሌነ ወማእከሌክሙ ከመ እለኒ ይፈቅዱ ይኅልፉ



### ክፍል ፹፪ ፡ ስለ ፈሪሳውያን መጠቃቀስ ።

ፈሪሳውያንም ሁሉ ይህን ሰምተው ተጠቃቀሱበት ፲፬
ገንዘብ ወዳጆች ናቸውና ፡ ማቴ ፳፫ ፲፬-፲፭ ፡ ቲቶ
፩ ፲፩ ።
እርሱም እናንተስ ለሰው ይምሰል ትመጻደቃላችሁ ፲፭
እግዚአብሔር ግን ልቡናችሁን ያውቃል ፡ በሰው
ዘንድ የከበረ በእግዚአብሔር የተዋረደ የተናቀ
ነውና ፡ ምዕ ፲፰ ፱ ፡ ምሳ ፮ ፲፮-፲፯ ፡ ሉቃ ፲ ፳፪ ።
ኦሪትም ነቢያትም ከጥንት ጀምሮ እስከ ዮሐንስ ፲፮
ድረስ ስለ እግዚአብሔር መንግሥት አስተማሩ
ሁሉም ስለ እሷ ይገፋል ፡ ማቴ ፲፩ ፲፪-፲፫ ።
ነገር ግን ከኦሪትና ከነቢያት አንዲት ቃል ከምት ፲፯
ወድቅ ሰማይና ምድር ቢያልፍ ይቀላል ፡ ማቴ ፭
፲፰ ፡ ኢሳ ፵ ፰ ፡ ፩ ጴጥ ፩ ፳፭ ።
ሚስቱን ፈትቶ ሌላይቱን ያገባ ሁሉ አመነዘረ ፡ የተፈ ፲፰
ታችውንም ያገባ አመንዝራ ነው ፡ ባሏ የፈታት
ሴትም ሌላ ባል ካገባች አመነዘረች ፡ ማቴ ፭ ፴፪ ፡
፲፱ ፰-፱ ፡ ፩ ቆሮ ፯ ፲ ።

### ክፍል ፹፫ ፡ ስለ አንድ ባለጸጋና ስለ አልአዛር ።

አንድ ባለጸጋ ሰው ነበረ ፡ ነጭ ሐር ብጫ ሐር ቀጫ ፲፱
ጭን ልብስ ይለብስ ነበር ፡ ሁለ ጊዜም ደስ ይለው
ነበር ፡ ራእ ዮሐ ፲፰ ፲፪ ።
በቍስለ ሥጋ ታሞ ከባለ ጸጋው ደጅ የወደቀ ሰው ፳
አልአዛር የሚባል አንድ ድኻም ነበር ፡ ዕብ ፲፩
፴፮-፴፯ ።
ከበለ ጸጋው ማእድ የሚወድቀውንም ፍርፋሪ ሊመ ፳፩
ገብ ይሻ ነበር ፡ ውሾችም እየመጡ ቍስሉን ይል
ሱት ነበር ፡ ማቴ ፲፭ ፳፯ ።
ከዚህም በኋላ ያ ድኻ ሞተና መላእክትም ወደ አብ ፳፪
ርሃም እቅፍ ወሰዱት ፡ ማቴ ፰ ፲፩ እብ ፩ ፲፬
ያዕ ፪ ፭ ።
ባለጸጋውም ሞተና ተቀበረ ፡ በሲኦልም በስቃይ ፳፫
ላይ ሳለ ዓይኖቹን አሻቅቦ አብርሃምን በሩቅ አየው
አልአዛርንም በእቅፉ አየው ።
አባቴ አብርሃም ! እዘንልኝ ፡ በዚች እሳት እጅግ ተሠ ፳፬
ቃይቻለሁና ፡ጣቱን ከውኃ ነክሮ መላሴን ያቀዝቅ
ዝልኝ ዘንድ አልአዛርን ላከው ብሎ ተጣራ ፡ ዘካ
፲፬ ፲፪ ፡ ኢሳ ፷፮ ፳፬ ።
አብርሃምም ፡ ልጄ ! በሕይወትህ እንደ ተደላደልክ ፳፭
እንደ ተቀማጠልክ አስብ ፡ አልአዛር ግን እንዲሁ በች
ጋር እንደ ነበረ አስብ ፡ አሁን ግን እንዲሁ እሱ በዚህ
ደስ ይለዋል አንተም መከራን ትቀበላለህ ኢዮ ፳፩
፲፫ ፡ መዝ ፲፯ ፲፬-፲፭ ፡ መዝ ፵፱ ፲፪-፲፱ ።
ከዚህም ሁሉ ጋር ከወዲህ ወዲያ ሊያልፉ የሚሹ ፳፮
ወደ እናንተ ሊመጡ እንዳይችሉ ፡ ከእናንተ ወገን

እምለፌ ኢይክህሉ መጺአ ኀቤክሙ ፣ ወእለሂ እመ
ንገሌክሙ ኢይዕድዉ ኀቤነ ።
፳፯ ወይቤሎ እስእለከ አባ፡አብርሃም ትፈንዎ ለአልአዛር
ቤተ አቡየ ።
፳፰ እስመ ሀለዉ ኃምስቱ አኀውየ ይንግሮሙ ወይስምዑ
ወኢይምጽኡ እሙንቱሂ ውስተ ዛቲ ብሔረ ሕማም ።
፳፱ ወይቤሎ አብርሃም በሙ ሙሴ ወነቢያት ኪያሆሙ
ለይስምዑ ።

፴ ወይቤሎ አልቦ አባ አብርሃም አሐዱ እምነ ምው
ታን ለእመ ኢሖረ ኀቤሆሙ ወለእመ ኢነገሮሙ
ኢየአምኑ ወኢይኔስሑ ።
፴፩ ወይቤሎ አብርሃም ለእመሰኬ ሙሴሃ ወነቢያተ ኢይ
ሰምዑ እመኒ ቦ ዘተንሥአ እምዉታን ኢይሰምዕዎ
ወኢየአምንዎ ።

ምዕራፍ ፲ወ፯ ።

<u>ክፍል ፹ወ፬ ፡ በእንተ ምጽአተ መንሱት ።</u>

፩ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ለአርዳኢሁ ግብር
ይመጽእ መንሱት ፣ ወባሕቱ አሌ ሎቱ ለዘያመጽእ
ለመንሱት እምኀቤሁ ።
፪ እምኀየሶ ይእስሩ በክሳዱ ማኅረፀ አድግ ወያስጥምዎ
ውስተ ቀላየ ባሕር እምያስሕቶ ለአሐዱ እምእሉ
ንኡሳን ።
፫ ዑቁ ርእሰክሙ ለእመ አበሰ ለከ እኁከ ገሥፆ በባ
ሕቲትከ ፡ ወለእመሰ ነስሐ ኅድግ ሎቱ ።
፬ ወእመኒ ስብዐ ለለዕለቱ አበሰ፣ ወስብዐ ለለዕለቱ ተጋ
ነየ ኅድግ ሎቱ ።

<u>ክፍል ፹ወ፭ ፡ በእንተ ኃይለ ሃይማኖት ።</u>

፭ ወይቤልዎ ሐዋርያት ለእግዚእነ ወስከነ ሃይማኖተ ።

፮ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ እመ ብክሙ ሃይማ
ኖት መጠነ ኅጠተ ሰናፔ ወትብልዋ ለዛቲ ሰግላ
ተመልሒ እምሥርውኪ ወተተከሊ ውስተ ባሕር
ትትኤዘዝ ለክሙ ።
፯ ወመኑ እምኔክሙ ዘቦ ገብር ሐረሳዊ ወእመኒ ኖላዊ
ወአቲዎ እምወፍሩ ይብሎ እግዚኡ ዕርግ ወነዓ
ርፍቅ ምስሌየ ።

፰ አኮኑ ይብሎ አስተዳሉ ሊተ ዘእዴረር ወቅንት ወመ
ጥወኒ እስከ እበልዕ ወእሰቲ፣ ወእምዝ ብላዕ ወስ
ተይ አንተሂ ።
፱ ቦኑ እንጋ ምዝጋና ለውእቱ ገብር ለእመ ገብረ ዘአ
ዘዘ እግዚኡ ።
፲ ከማሁኬ አንትሙኒ ገቢረክሙ ኵሎ ዘአዘዝኩክሙ



የሆኑትን ወደ እኛ እንዳይሻገሩ ፡ በእኛና በእናንተ
መካከል ታላቅ ገደል ይከለክለናል ፡ ፪ ተሰ. ፩ ፱ ።
እርሱም እንዲህ አለው አባቴ አብርሃም ! አልአዛርን ፳፯
ወደ አባቴ ቤት ትልከው ዘንድ እለምንሃለሁ ።
አምስቱ ወንድሞቼን አሉና እነሱም ሰምተው ወደ ፳፰
ዚች የሥቃይ ቦታ እንዳይመጡ ይንገራቸው ።
አብርሃምም ሙሴና ነቢያት አሏቸው እነሱን ይስሙ ፳፱
አለው ፡ ኢሳ. ፰ ፳ ፡ ዮሐ. ፭ ፴፱ ፡ ግ. ሐ. ፲፭ ፳፩ ፡
፪ ጢሞ ፫ ፲፮ ።
አባ አብርሃም የለም ፡ ከሙታን አንዱ ከልሄደና ካል ፴
ነገራቸው አያምኑም ንስሐም አይገቡም ።

አብርሃምም ሙሴንና ነቢያትን ካልሰሙማ ከሙታን ፴፩
ተለይቶ የተነሣ ቢኖርም አይሰሙትም አያምኑትም
አለው ፡ ዮሐ. ፲፩ ፵፬-፵፯ ፡ ፲፪ ፱-፲ ።

ምዕራፍ ፲፯ ።

<u>ክፍል ፹፬ ፡ ስለ ፈተና መምጣት ።</u>

ጌታ ኢየሱስ ለደቀ መዛሙርቱ እንዲህ አላቸው ፩
መከራ ግድ ይመጣል ፡ ነገር ግን ምክንያት ሆኖ መከ
ራን ለሚያመጣት ሰው ወዮለት ! ።
ከእሊህ ከታናናሾቹ አንዱን ከሚያስተው የአህያን ፪
ወፍጮ በአንገቱ አስረው ወደ ጥልቅ ባሕር ቢያሰ
ጥሙት በተሻለው ነበር ፤ ማቴ. ፲፰ ፮ ፡ ማር. ፱ ፵፪ ።
ራሳችሁን ዕወቁ ፡ ወንድምህ አንተን ቢበድልህ ብቻ ፫
ህን ሆነህ ምከረው ፡ ቢጸጸትም ይቅር በለው ፡ ዘሌዋ.
፲፱ ፲፯ ፡ ማቴ ፲፰ ፲፭ ።
በየቀኑ ሰባት ጊዜ ቢበድልና በየቀኑም ሰባት ጊዜ ፬
ቢጸጸትም ይቅር በለው ።

<u>ክፍል ፹፭ ፡ ስለ ሃይማኖት ኃይል ።</u>

ሐዋርያትም ጌታን ሃይማኖትን ጨምርልን አሉት ፡ ፭
ማር. ፱ ፳፬ ።
ጌታ ኢየሱስም እንዲህ አላቸው ፣ የሰናፍጭ ቅንጣት ፮
ታህል ሃይማኖት ብትኖራችሁ ይህቺን ሾላ ከሥርሽ
ተነቅለሽ በባሕር ውስጥ ተተከዪ ብትሏት ትታዘዝላ
ችኋለች ፡ ማቴ ፲፯ ፳-፳፩ ፡ ማር. ፱ ፳፫ ።
አራሽ ፡ ወይም ከብት ጠባቂ አገልጋይ ያለው ከእና ፯
ንተ ማነው ? ከተሠማረበት በተመለሰ ጊዜ ጌታው
ና ፈጥነህ ወደዚህ ውጣና ከእኔ ጋር ተቀመጥ ራት
ብላ ይለዋልን ? ።
ራቴን አዘጋጅልኝና እስክበላ እስክጠጣ ድረስ ፰
ታጥቀህ አሳልፍልኝ ከዚህ በኋላ አንተም ብላ ጠጣ
የሚለው አይደለምን ? ማር. ፱ ፳፫ ።
እንግዲህ ጌታው ያዘዘውን ቢያደርግ ለዚያ አገልጋይ ፱
ምስጋና አለውን ? ።
እንዲህም እናንተ ያዘዝኋችሁን ሁሉ አድርጋችሁ ፲

በሉ አግብርት ጽሩዓን ንሕነ ወዘይደልወነ ለገቢር ገበርነ ።

ክፍል ፹ወ፮ ፡ በእንተ ዐሠርቱ እለ ለምጽ ።

፲፩ ወእምዝ እንዘ የሐውር ኢየሩሳሌም ኀለፈ ማእከለ ሰማርያ ወገሊላ ።
፲፪ ወእንዘ ይበውእ አሐተ ሀገረ ተቀበልዎ ዐሠርቱ ዕደው እለ ለምጽ ወቆሙ እምርኁቅ ።
፲፫ ወአውየዉ ወይቤሉ ኢየሱስ ሊቅ ተሠሃለነ ።
፲፬ ወርእዮሙ ወይቤሎሙ ሑሩ ኀበ ካህን ወአፍትኑ ርእሰክሙ ወእንዘ የሐውሩ ነጽሑ ።
፲፭ ወርእዮ አሐዱ እምኔሆሙ ከመ ነጽሐ ተመይጠ እንዘ የአኵቶ ለእግዚአብሔር በዐቢይ ቃል ።
፲፮ ወሰገደ ታሕተ እገሪሁ ለእግዚእ ኢየሱስ በገጹ ወአእኰቶ ወሳምራዊ ውእቱ ብእሲሁ ።
፲፯ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ አኮኑ ዐሠርቱ እሙንቱ እንትሙ እለ ነጽሑክሙ አይቴኑ እንከ ተስዐቱ ? ።
፲፰ ሎሙሰ ተሰእኖሙኑ ተመይጦ ወአእኵቶቶ ለእግዚአብሔር ዘእንበለ ዝንቱ ዘካልእ ሕዝቡ ።
፲፱ ወይቤሎ ተንሥእ ወሑር ሃይማኖትከ አሕየወተከ ።

ክፍል ፹ወ፯ ፡ በእንተ ምጽአተ መንግሥተ እግዚአብሔር ፡

፳ ወተሰእልዎ ፈሪሳውያን ወይቤልዎ ማእዜ ትመጽእ መንግሥተ እግዚአብሔር ፡ ወአውሥአ ወይቤሎሙ ኢትመጽእ መንግሥተ እግዚአብሔር በተዐቅቦ ።
፳፩ ወኢይብልዋ ነያ ዝየ ወነያ ከሐከ ፡ መንግሥተ እግዚአብሔርሰ ነያ ማእከሌክሙ ይእቲ ።
፳፪ ወይቤሎሙ ለአርዳኢሁ ይመጽእ መዋዕል አመ ትፈትዉ ትርአዩ አሐተ እምነ መዋዕሊሁ ለወልደ እጓለ እመሕያው ፡ ወኢትሬእዩ ።
፳፫ ወለእመ ይብሉክሙ ነዋ ዝየ ወነዋ ከሐከ ኢትፃኡ ወኢትዴግኑ ።
፳፬ እስመ ከመ መብረቅ ዘይበርቅ ወያበርህ እምአጽናፈ ሰማይ እስከ አጽናፈ ሰማይ ከማሁ ውእቱ ምጽአቱ ለወልደ እጓለ እመሕያው ።
፳፭ ወባሕቱ እምቅድመ ዝንቱ ኵሉ ብዙኀ የሐምም ፡ ወትሜንኖ ወታሜክሮ ዛቲ ትውልድ ።
፳፮ ወበከመ ኮነ በመዋዕሊሁ ለኖኅ ከማሁ ይከውን በምጽአቱ ለወልደ እጓለ እመሕያው ።



እኛ ሥራ ፈቶች ባሮች ነን ለመሥራትም የሚገባንን ሥራን በሉ ፡ ኢዮ. ፳፪ ፫ ፡ መዝ. ፲፮ ፪ ።

ክፍል ፹፮ ፡ ስለ ዐሥሩ ለምፃሞች ።

ከዚህ በኋላ ወደ ኢየሩሳሌም ሲሄድ በገሊላና በሰ ፲፩
ማርያ መካከል አለፈ ፡ ዮሐ. ፬ ፬ ።
ወደ አንዲት አገርም ሲገባ ለምጽ የያዛቸው ዐሥር ፲፪
ወንዶች ተቀበሉትና ራቅ ብለው ቆሙ ፡ ሌዋ. ፲፫
፵፮ ፡ ዘኍ. ፭ ፪ ።
ድምፃቸውንም ከፍ አድርገው ኢየሱስ መምህር ! ፲፫
እዘንልን አሉ ፡ መዝ. ፻፯ ፲፱ ።
ልመናቸውንም ሰምቶ ወደ ካህን ሂዱና ራሳቸሁን ፲፬
አንጹ አላቸው ፡ ሲሄዱም ነጹ ፡ ዘሌዋ. ፲፫ ፪ ፡ ፵፭
፵፮ ፡ ፲፬ ፪ ።
ከእነሱም አንዱ እንደ ነጻ በየ ጊዜ በታላቅ ቃል እግ ፲፭
ዚአብሔርን እያመሰገነ ተመለሰ ፡ መዝ. ፻፫ ፩ ።
በግንባሩም ወድቆ ከጌታ ኢየሱስ እግር በታች ሰገ ፲፮
ደና አመሰገነ ፡ ሰውየውም ሳምራዊ ነበር ።
ጌታ ኢየሱስም መልሶ የነጻችሁት እናንት ዐሥር ፲፯
አልነበራችሁምን ? እንግዲያ ዘጠኙ የት አሉ ? አለው ።

ወገኑ ሌላ ከሆነ ከዚህ ሰው በቀር ለእነዚያ ተመልሶ ፲፰
እግዚአብሔርን ማመስገን ተሳናቸውን ? ።
ተነሥና ሂድ ሃይማኖትህ አዳነችህ አለው ፡ ምዕ ፯ ፲፱
፶ ፤ ፰ ፡ ፵፰ ።

ክፍል ፹፯ ፡ ስለ እግዚአብሔር መንግሥት መምጣት ፡

ፈሪሳውያንም የእግዚአብሔር መንግሥት መቼ ትመ ፳
ጣለች ? ብለው ጠየቁት ፡ እርሱም መልሶ እንዲህ
አላቸው ፡ የእግዚአብሔር መንግሥት በመጠባበቅ
አትመጣም ፡ ዮሐ. ፲፰ ፴፮ ፡ ፩ ቆሮ. ፬ ፳ ።
እዚህ ናት ወይም እዚያ ናት አይሏትም ፡ የእግዚ ፳፩
አብሔር መንግሥትስ እነኋት በመካከላችሁ ናት ፡
ማቴ. ፳፬ ፳፫ ፡ ማር. ፲፫ ፳፩ ።
ደቀ መዛሙርቱንም እንዲህ አላቸው ከሰው ልጅ ፳፪
ቀኖች አንዲቱን ታዩ ዘንድ የምትመኙበት ወራት
ይመጣል ፡ ግን አታዩም ፡ ማቴ. ፱ ፲፮ ።
ከዚህ ነው ወይም ከዚያ ነው ቢሏችሁ አትውጡ ፳፫
አትፈልጉ ፡ ምዕ. ፳፩ ፰ ፡ ፩ ዮሐ. ፬ ፩ ።
መብረቅ ብልጭ ብሎ ከዳር እስከ ዳር እንደሚያበራ ፳፬
የሰው ልጅ አመጣጡ እንዲሁ ነውና ፡ ማቴ. ፳፬ ፳፯ ።

ነገር ግን ከዚህ ሁሉ አስቀድሞ ብዙውን መከራ ይቀ ፳፭
በላል ፤ ይህችም ትውልድ ትንቀዋለች ትፈታተነውም
አለች ፡ ማቴ. ፲፮ ፳፩ ።
በኖኅ ዘመን እንደሆነው የሰው ልጅ በሚመጣበትም ፳፮
ጊዜ እንዲሁ ይሆናል ፡ ዘፍ. ፯ ፩ ።

፳፯ ወበከመ ከነ እንዘ ይበልዑ ወይሰትዩ ወያወስቡ ወይ
ትዋሰቡ እስከ አመ በአ ኖኅ ውስተ ንፍቀ ታቦት
ወመጽአ ማየ አይኅ ወአጥፍአ ኵሎ ኅቡረ ።
፳፰ ወበከመ ከነ በመዋዕሊሁ ለሎጥ እንዘ ይበልዑ ወይ
ሰትዩ ፡ ወየሐንጹ ወይተክሉ ወይሠይጡ ወይሣየጡ ።
፳፱ እስከ አመ ዕለተ ወፅአ ሎጥ እምሰዶም ወአዝነመ
እግዚአብሔር እሳተ ወተየ እምሰማይ ወአጥፍአ
ኵሎ ።
፴ ከማሁ ውእቱ ምጽአቱ ለወልደ እጓለ እመሕያው
ኢይትዐወቅ ።
፴፩ ይእተ አሚረ ዘሀሎ ውስተ ናሕስ ወንዋዩ ውስተ
ቤት ኢይረድ ይንሣእ ፤ ወዘሂ ገዳመ ሀሎ ኢይግባእ
ድኅሬሁ ።
፴፪ ተዘከርዋ ለብእሲተ ሎጥ ።
፴፫ ዘይፈቅድ ያድኅና ለነፍሱ ለይግድፋ ፡ ወዘሰ ገደፋ
ለነፍሱ በእንቲአየ ያሐይዋ ።
፴፬ እብለክሙ በይእቲ ሌሊት ክልኤቱ ይሰክቡ ውስተ
አሐዱ ዓራት አሐደ ይነሥኡ ወካልአ የኃድጉ ።

፴፭ ወክልኤቲ የኀርፃ ውስተ አሐቲ ማኅረፅ አሐተ ይነ
ሥኡ ወካልእታ የኅድጉ ።
፴፮ ወክልኤቱ ይሄልዉ ውስተ አሐዱ ገራህት አሐደ
ይነሥኡ ወካልአ የኅድጉ ።
፴፯ ወአውሥኡ ወይቤልዎ በአይቴኑ እግዚኦ ፡ ወይቤ
ሎሙ ኀበ ሀሎ ገደላ ህየ ይትጋብኡ አንስርት ።

ምዕራፍ ፲ወ፰ ፤

ክፍል ፹ወ፫ ምሳሌ በእንተ አሐዱ መኰንን ።

፩ ወይቤሎሙ በምሳሌ ከመ ዘልፈ ይጸልዩ ወኢይ
ትሀከዩ ።

፪ ወይቤሎሙ ሀሎ በአሐቲ ሀገር አሐዱ መኰንን
ዘኢይፈርህ እግዚአብሔርሃ ወኢየኃፍር ሰብአ ።
፫ ወሀለወት አሐቲ ዕቤርት በይእቲ ሀገር ወክነት ትመ
ጽእ ኀቤሁ ወትብሎ ኰንነኒ እምእድውየ ፡ አበያ ወአ
ንዳያ ።
፬ ወእምዝ ሐለየ በልቡ ወይቤ እመ ኢይፈርሆ ለእግ
ዚአብሔር ወኢየኀፍር ሰብአ ፡ ከመ ኢታንጥየኒ ዛቲ
ዕቤር እትቤቀል ላቲ ከመ ኢትምጻእ ወኢታስርሐኒ
ዘልፈ ።
፭ ወይቤሎሙ እግዚእነ ስምዑ ዘይቤ መኰንነ ዐመፃ ።

፮ ኢይፈትሕኑ እንከ እግዚአብሔር ለኅሩያኒሁ እለ
ይግዕሩ ኀቤሁ መዓልተ ወሌሊተ ወይትዔገሦሙኑ ።

፯ አወ እብለክሙ ከመ ይፈትሕ ሎሙ ፍጡነ ፡ ወባሕቱ



ኖኅ ወደ መርከብ እስኪገባ ድረስ ይበሉ ይጠጡ ፳፯
ያገቡ ይጋቡ እንደ ነበረ የጥፋት ውኃም መጥቶ
ሁሉን አንድ አድርጎ እንደ አጠፋ ፡ ዘፍጥ. ፯ ፯ ።
በሎጥ ዘመንም ይበሉ ይጠጡ ቤት ይሠሩ ተክል ፳፰
ይተክሉ ይሸጡ ይገዙ እንደነበረ ፡ ዘፍ. ፲፱ ፩ ።
ሎጥ ከሰዶም እስከ ወጣበት እግዚአብሔርም ከሰማይ ፳፱
እሳትንና ዲንን አዝንሞ ሁሉን እንዳጠፋበት ፤ ዘፍ
፲፱ ፲፭ ።
የሰውም ልጅ አመጣጡ እንዲሁ ነው ፡ አይታወ ፴
ቅም ፡ ማቴ. ፳፬ ፫ ፡ ራ. ዮ. ፩ ፯ ።
ያን ጊዜ በሰገነት ያለ ገንዘቡም በምድር ቤት የሆ ፴፩
ነበት ሰው ሊያነሣ አይውረድ ፡ በዱር ያለም ወደ
ኋላው አይመለስ ፡ ማቴ. ፳፬ ፲፯ ።
የሎጥን ሚስት አስቧት ፡ ዘፍጥ. ፲፱ ፳፯ ። ፴፪
ነፍሱን ሊያድናት የሚወድ ይጣላት ፡ ስለ እኔም ነፍ ፴፫
ሱን የጣላት ያድናታል ፡ ምዕ. ፱ ፳፬ ፡ ማቴ. ፲ ፴ ።
እላችኋለሁ ሁለት ሰዎች በአንድ አልጋ ይተኛሉ ፡ ፴፬
አንዱን ይወስዳሉ ፡ ሁለተኛውን ይተዋሉ ፡ ማቴ. ፳፬
፵-፵፩ ።
ሁለት ሴቶችም በአንድ ወፍጮ ይፈጫሉ ፡ አንዲቱን ፴፭
ይወስዳሉ ሁለተኛይቱን ይተዋሉ ።
ሁለት ሰዎች በአንድ እርሻ ላይ ይኖራሉ ፡ አንዱን ፴፮
ይወስዳሉ ፡ ሁለተኛውን ይተዋሉ ።
እነሱም መልሰው አቤቱ በየት ነዋ? አሉት እርሱም ፴፯
ጥንብ ካለበት አሞሮች ከዚያ ይሰበሰባሉ አላቸው
ኢዮ. ፴፱ ፴ ፡ ዕንበ ፩ ፰ ፡ ማቴ. ፳፬ ፳፰ ።

ምዕራፍ ፲፰ ።

ክፍል ፹፫ ፡ ምሳሌ ስለ አንድ ፈራጅ ።

ዘወትር እንዲጸልዩና እንዳይሰንፉ በምሳሌ አስተማ ፩
ራቸው ፡ ዘፍ. ፴፪ ፱-፲ ፡ መዝ. ፶፭ ፲፮-፲፯ ፡ ሮሜ.
፲፪ ፲፪ ።
በአንዲት አገር እግዚአብሔርን የማይፈራ ሰውን የማ ፪
ያፍር አንድ ዳኛ ነበር ።
በዚያች አገር አንዲት ባልቴት ነበረችና ወደርሱ ፫
እየመጣች ከባላጋራዬ ፍረድልኝ ትለው ነበር ፡ እንቢ
አላት አዘገያትም ፡ ዘፀአ. ፳፪ ፳፪-፳፫ ።
ከዚህ በኋላ በልቡ አሰበ እግዚአብሔርንም ባልፈራ ፬
ሰውንም ባላፍር ይህቺ ባልቴት እንዳትዘበዝበኝ ዘወ
ትር እየመጣች እንዳታዳክመኝ እፈርድላታለሁ አለ ፡
መሳ. ፲፮ ፲፯ ፡ ምዕ. ፲፩ ፯-፱ ።
ጌታችንም እንዲህ አላቸው ዐመፀኛው ዳኛ ያለውን ፭
ስሙ ።
እንግዲያስ እግዚአብሔር በመዓልትም በሌሊትም ፮
ወደርሱ ለሚጮሁ ለመረጣቸው አይፈርድላቸውምን
ወይስ ቸል ይላቸዋልን? ፩ ሳሙ. ፳፬ ፲፪ ።
ፈጥኖ እንደሚፈርድላቸው በእውነት እላችኋለሁ ፯

ወልደ እጓለ እመሕያው መጺኦ ይረክቡኑ እንጋ ሃይማኖተ በዲበ ምድር ።

## ክፍል ፹ወ፱፡ በእንተ ፈሪሳዊ ወመጸብሐዊ ።

፱ ወይቤሎሙ ለእለ ያጸድቁ ርእሶሙ ወይሜንኑ ቢጸሙ ወመሰለ ሎሙ ከመዝ ።
፲ ክልኤቱ ዕደው ዐርጉ ቤተ መቅደስ ይጸልዩ፡ አሐዱ ፈሪሳዊ ወካልኡ መጸብሐዊ ።
፲፩ ወቆመ ፈሪሳዊ ወጸለየ ወይቤ፡ አአኰተከ እግዚኦ ዘኢረሰይከኒ ከመ ባዕዳን ሰብእ ኃያድያን ወዓማፅያን ወእለ የሐውሩ ብእሲተ ብእሲ ወኢከመ ዝንቱ መጸብሐዊ ።
፲፪ አንሰ እጼውም ሰኑየ መዋዕለ በሰናብት፡ ወአበውእ ዐሥራተ እዴሁ ለኵሉ ዘአጥረይኩ ።
፲፫ ወመጸብሐዊሰ ቆመ እምርኁቅ ወኢፈቀደ ያንሥእ አዕይንቲሁ ላዕለ ውስተ ሰማይ ወጐድአ እንግድዓሁ ወይቤ ሥረይ ሊተ እግዚኦ እስመ አነ ኃጥእ ዘኢይደልወኒ እቁም ውስተ መካነ መቅደስከ ።
፲፬ ወእብለክሙ አተወ ቤቶ ዝንቱ እንዘ ይጸድቅ እምዝንቱ፡ እስመ ኵሉ ዘአዕበየ ርእሶ የኀስር ወዘአትሐተ ርእሶ ይከብር ።

## ክፍል ፺፡ በእንተ በርከቱ ሕፃናት ።

፲፭ ወአምጽኡ ኀቤሁ ሕፃናተ ይግሥሦሙ ወያንብር እዴሁ ላዕሌሆሙ ወርእዮሙ አርዳኢሁ ገሠፅዎሙ ።
፲፮ ወጸውዖሙ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ ኅድጉ ሕፃናተ ይምጽኡ ኀቤየ ወኢትክልእዎሙ እስመ ለዘከመ እሉ ይእቲ መንግሥተ እግዚአብሔር ።
፲፯ አማን እብለክሙ ዘኢተቀበላ ለመንግሥተ እግዚአብሔር ከመ ሕፃናት ኢይበውኣ ።

## ክፍል ፺ወ፩፡ በእንተ ባዕል ዘተስእሎ ።

፲፰ ወተስእሎ አሐዱ መልአክ ወይቤሎ ሊቀ ኄር ምንተ ሠናየ ገቢርየ እረክብ ሕይወተ ዘለዓለም ።
፲፱ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ለምንት ትብለኒ ኄር አልበ ኄር ዘእንበለ አሐዱ እግዚአብሔር ።
፳ ተአምር ትእዛዛቲሁ ኢትቅትል ነፍሰ፤ ወኢትሑር ብእሲተ ብእሲ፡ ወኢትዘሙ፤ ወኢትስርቅ፡ ወኢትኩን ስምዐ በሐሰት፡ ወአክብር አባከ ወእመከ ።



ነገር ግን የሰው ልጅ በመጣ ጊዜ በምድር ላይ እምነትን ያገኝ ይሆን? ኤር. ፳ ፲፪ ፡ ፪ ተሰ. ፩ ፯ ፡ ምዕ. ፲፯ ፳፪ ፡ ሮሜ ፲፯ ፳ ።

## ክፍል ፹፱ ፡ ስለ ፈሪሳዊውና ስለ ቀራጩ ።

ራሳቸውን ለሚያመጻድቁ በልንጀራቸውን ለሚንቁ ሰዎች እንዲህ ብሎ መሰለላቸው ፡ ምሳ. ፴ ፲፪ ። ፱
ሁለቱ ሰዎች ሊጸልዩ ወደ ቤተ መቅደስ ገቡ አንዱ ፈሪሳዊ ሁለተኛው ቀራጭ ነበር፡ ማቴ. ፯ ፳-፴፯ ። ፲
ፈሪሳዊውም ቆመና እንዲህ ብሎ ጸለየ ፡ አቤቱ! እንደ ሌሎች ሰዎች እንደ ቀማኞች እንደ በመፀኞች ወደ ሰው ሚስት እንደሚሄዱ ወይም እንደዚህ ቀራጭ ያላደረግኸኝ አመሰግንሃለሁ፡ ኢሳ ፩ ፲፭ ፡ ኢሳ. ፶፰ ፪ ፡ ማቴ፳ ፩ ፡ ራ. እ. ፫ ፲፯ ። ፲፩
እኔ በየሳምንቱ ሁለት ቀን እጾማለሁ ከገኘሁትም ሁሉ ከዐሥር አንድ እሰጣለሁ ። ፲፪
ቀራጩ ግን ራቅ ብሎ ቆመ ዓይኖቹን ወደላይ ወደ ሰማይ ሊያነሣ አልወደደም ደረቱንም እየደቃ እኔ በመመስገኛህ ቦታ መቆም የማይገባኝ ኃጢአተኛ ነኝና ይቅር በለኝ አለ፡ መዝ. ፵ ፲፪ ፡ መዝ. ፶፩ ፫ ። ፲፫
ከዚያኛው ይልቅ ይህ ጻድቅ ሆኖ ወደ ቤቱ እንደ ተመለሰ እነግራችኋለሁ ራሱን ከፍ ከፍ ያደረገ ይዋረዳል፤ ራሱን ዝቅ ዝቅ ያደረገ ይከብራልና፡ ኢዮ. ፳፪ ፳፱ ፤ ኢሳ. ፶፩ ፪፡ ማቴ. ፳፫ ፲፪፡ ያዕ. ፬ ፯ ፡ ፩ ጴጥ. ፭ ፭ ። ፲፬

## ክፍል ፺ ፡ ሕፃናትን ስለ መባረኩ ።

እጁን በላያቸው ጭኖ ይዳስሣቸው ዘንድ ሕፃናትን ወደርሱ አመጡ፡ ደቀ መዛሙርቱም አይተው ገሠጿቸው፡ ኢሳ. ፵፱ ፳፪ ፤ ፲፱ ፲፫-፲፭ ። ፲፭
ጌታ ኢየሱስም ጠርቶ ተው ሕፃናት ወደ እኔ ይምጡ አትከልክሏቸው፡ የእግዚአብሔር መንግሥት እንደነዚህ ላሉት ናትና አላቸው፡ ምሳ. ፰ ፲፯ ። ፲፮
እውነት እላችኋለሁ የእግዚአብሔርን መንግሥት እንደ ሕፃናት ያልተቀበላት አይገባበትም፡ ማር. ፲ ፲፮ ፩ ቆሮ. ፲፭ ፳ ። ፲፯

## ክፍል ፺፩ ፡ ስለ ጠየቀው ባለጸጋ ።

አንድ አለቃም ቸር መምህር! ምን ሥራ ሠርቼ የዘለዓለም ሕይወትን አገኛለሁ? አለው፡ ማቴ. ፲፱ ፲፯ ። ፲፰
ጌታ ኢየሱስም እንዲህ አለው፡ ለምን ቸር ትለኛለህ? ካንድ እግዚአብሔር በቀር ቸር የለም ። ፲፱
ትእዛዛቶቹን ታውቃለህ፡ ነፍስ አትግደል፡ ወደ ሰው ሚስት አትሂድ፡ አትስስን፡ አትስረቅ፡ በሐሰት አትመስክር አባትህንና እናትህን አክብር፡ ዘፀ. ፳ ፲፪፡ ሮሜ. ፲፫ ፱፡ ኤፌ. ፯ ፪ ። ፳

፳ ወይቤሎ ዘንተሰ ኵሎ ዐቀብኩ እምንእስየ እስከ ይእዜ ።

፳፩ ወሰሚዖ ዘንተ እግዚእ ኢየሱስ ይቤሎ አሐቲ ተርፈተከ ሑር ወሢጥ ኵሎ ዘብከ ንዋየ ወሀብ ለነዳያን ፡ ወትረክብ መዝገበ ዘበሰማያት ወነዓ ትልወኒ ።

፳፪ ወሰሚዖ ዘንተ ተከዘ ፈድፋደ እስመ ብዕል ውእቱ ጥቀ ወብዙኅ ጥሪቱ ።

፳፫ ወርእዮ እግዚእ ኢየሱስ እንዘ ይቴክዝ ብዙኀ ፡ ይቤ ዕፁብ ለእለ ብሙ ንዋይ በዊእ ውስተ መንግሥተ እግዚአብሔር ።

፳፬ ይቀልል ይኅልፍ ገመል እንተ ስቊረተ መርፍእ እምባዕል ይባእ ውስተ መንግሥተ እግዚአብሔር ።

፳፭ ወይቤሉ እለ ሰምዑ መኑ እንከ ይክል ድኂነ ።

፳፮ ወይቤሎሙ ዘበኀበ ሰብእ ይሰአን በኀበ እግዚአብሔር ይትከሀል ።

## ክፍል ፺ወ፪ ፡ በእንተ ተላውያነ ኢየሱስ ።

፳፯ ወይቤሎ ጴጥሮስ ናሁኬ ንሕነ ኅደግነ ኵሎ ወተሉናከ ፡ ምንተ እንጋ ንረክብ ።

፳፰ ወይቤሎሙ አማን እብለክሙ አልቦ መኑሂ ዘየኀድግ ቤቶ ወአዝማዲሁ ወአኀዊሁ ወብእሲቶ ወውሉዶ በእንተ መንግሥተ እግዚአብሔር ።

፳፱ ወዘይትዐወይ ምእተ ምክዕቢተ በዝንቱ ዓለም ፡ ወበዓለምሰ ዘይመጽእ ሕይወተ ዘለዓለም ።

## ክፍል ፺ወ፫ ፡ በእንተ ሕማሙ ወሞቱ ።

፴ ወነሥኦሙ ለዐሠርቱ ወክልኤቱ ወይቤሎሙ ናሁ ነዓርግ ኢየሩሳሌም ወይትፌጸም ኵሉ ዘጽሑፍ ውስተ መጻሕፍተ ነቢያት ላዕለ ወልደ እጓለ እመሕያው ።

፴፩ ወይሜጥውዎ ለአሕዛብ ወይሳለቁ ላዕሌሁ ወይጼእልዎ ወይዌርቅዎ ።

፴፪ ወይቀሥፍዎ ወይቀትልዎ ወይትነሣእ በሣልስት ዕለት ፡

፴፫ ወእሙንቱሰ አልቦ ዘለበዉ እምዝ ይቤሎሙ እስመ ሥዉር ውእቱ ዝ ነገር እምኔሆሙ ወኢየአምሩ ዘይብል ።

## ክፍል ፺ወ፬ ፡ በእንተ ዕውር ዘኢያሪሆ ።

፴፬ ወእምዝ አልጺቆሙ ኢያሪሆ ሀሎ አሐዱ ዕውር ይነብር ውስተ ፍኖት ወይስእል ።

፴፭ ወሰሚዖ ድምፀ ሰብእ ዘየኀልፍ ይቤ ምንትኑ ዝ ዘእሰምዕ ።



ይህንስ ሁሉ ከልጅነቴ ጀምሮ እስከ ዛሬ ጠብቄ አለሁ አለው ። ፳

ጌታ ኢየሱስም ይህን ሰምቶ አንዲት ቀርታሃለች ሂድና ያለህን ሁሉ ሽጠህ ለውጠህ ለድኾች ስጥ ፡ በሰማያት ያለውን መዝገብ ታገኛለህ መጥተህም ተከተለኝ አለው ። ማቴ፡ ፲ ፳ ። ፩ ጢሞ፡ ፮ ፲፱ ። ፳፩

ይህንንም ሰምቶ እጅግ አዘነ እሱ ባለጸጋ ነበርና ሀብቱም ብዙ ነበርና ። ፳፪

ጌታ ኢየሱስም እጅግ ሲያዝን አይቶ እንዲህ አለ ፤ ገንዘብ ላላቸው ሰዎች ወደ እግዚአብሔር መንግሥት መግባት ጭንቅ ነው ። ፳፫

ባለጸጋ ወደ እግዚአብሔር መንግሥት ከሚገባ ይልቅ ግመል በመርፌ ቀዳዳ ቢያልፍ ይቀላል ። ፳፬

የሰሙትም እንግዲህ ማን ሊድን ይችላል ? አሉና ። ፳፭

በሰው ዘንድ የማይቻለው በእግዚአብሔር ዘንድ ይቻላል አላቸው ፡ ዘፍ፡ ፲፰ ፲፬ ። ኢዮ፡ ፵፪ ፪ ። ኤር፡ ፴፪ ፲፯ ። ዘካ፡ ፰ ፮ ። ፳፮

## ክፍል ፡ ፺፪ ስለ ኢየሱስ ተከታዮች ።

ጴጥሮስም እነሆ እኛ ሁሉን ትተን ተከተልንህ እንግዲህ ምን እናገኛለን ? አለው ። ማቴ፡ ፲፱ ፳፯ ። ፳፯

እሱም እንዲህ አላቸው ፤ እውነት እነግራችኋለሁ ቤቱን ፡ ዘመዶቹን ፡ ወንድሞቹን ፡ ሚስቱን ፡ ልጆቹን ስለ እግዚአብሔር የሚተው የለም ። ዘዳ፡ ፴፫ ፱ ። ፳፰

ከተወም በዚህ ዓለም መቶ ዕጽፍ ዋጋ የማይቀበል የለም ፡ በሚመጣውም ዓለም የዘለዓለም ሕይወትን ያገኛል ። ኢዮ፡ ፵፪ ፲፪ ። ማቴ፡ ፲፱ ፳፱ ። ራ፡ዮ፡ ፪ ፲፯ ። ፳፱

## ክፍል ፺፫፡ ስለ ሕማሙና ስለ ሞቱ ።

ዐሥራ ሁለቱንም ጠርቶ እንዲህ አላቸው ፡ እነሆ ወደ ኢየሩሳሌም እንወጣለን በነቢያት መጽሐፍ የተጻፈው ሁሉ በሰው ልጅ ላይ ይፈጸማል ። ማቴ፡ ፳ ፲፯ - ፲፱ ። ማር፡ ፲ ፴፪ - ፴፬ ። ፴

ለአሕዛብ አሳልፈው ይሰጡታል ይዘብቱበታል ይሰድቡታል ፡ ይተፉበታል ፡ መዝ፡ ፳፪ ፯ ። ኢሳ፡ ፶፫ ፯ ። ማቴ፡ ፳፯ ፪ ። ግ፡ ሐ፡ ፫ ፲፫ ። ፴፩

ይገርፉታል ፡ ይገድሉታል ፡ በሦስተኛዪቱም ቀን ይነሣል ። ዮሐ፡ ፪ ፲፱ ። ፴፪

እነሱ ግን ከተናገራቸው ያስተዋሉት የለም ፡ ይህ ነገር ከነሱ የተሠወረ ነበርና የሚለውንም አያውቁም ነበርና ። ማር፡ ፱ ፴፪ ። ዮሐ፡ ፲ ፮ ። ፴፫

## ክፍል ፺፬፡ ስለ ኢያሪሆው ዕውር ።

ከዚህም በኋላ ኢያሪሆ በደረሱ ጊዜ አንድ ዕውር በጐዳና ተቀምጦ ይለምን ነበር ። ማቴ፡ ፳ ፳፱-፴፫ ማር፡ ፲ ፵፮ - ፶፪ ። ፴፬

የሚያልፈው የሰው ድምፅ ሰምቶ ይህ የምሰማው ምንድር ነው ? አለ ። ፴፭

## ወንጌል ዘሉቃስ ፲፱ ።

፴፯ ወይቤልዎ ኢየሱስ ናዝራዊ የኀልፍ ።
፴፰ ወአውየወ ወይቤ ኢየሱስ ወልደ ዳዊት ተሠሃለኒ ።

፴፱ ወገሠፅዎ እለ ይመርሕዎ ከመ ያርምም ወአውየወ
ፈድፋደ ወይቤ ወልደ ዳዊት ተሣሃለኒ ።
፵ ወቆመ እግዚእ ኢየሱስ ወአዘዘ ያምጽእዎ ኀቤሁ ።

፵፩ ወበጺሖ ኀቤሁ ይቤሎ ምንተ ትፈቅድ እግበር ለከ፣
ወይቤሎ እግዚኦ ከመ ይርአያ አዕይንትየ ።
፵፪ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ርኢ፣ ሃይማኖትከ አሕ
የወተከ ።
፵፫ ወርእየ ሶቤሃ ወተለዎ ወአእኰቶ ለእግዚአብሔር፣
ወርእዮሙ ኵሉ ሕዝብ ሰብሕዎ ለእግዚአብሔር ።

### ምዕራፍ ፲ወ፱ ።

### ክፍል ፺ወ፭፣ በእንተ ዘኬዎስ መጸብሓዊ ።

፩ ወቦአ ኢያሪሆ እግዚእ ኢየሱስ ወአንሶሰወ ።
፪ ወናሁ ረከበ ብእሴ ዘስሙ ዘኬዎስ መልአኮሙ ለመ
ጸብሓን ወበዕል ውእቱ ።
፫ ወየኃሥሥ ይርአዮ ለእግዚእ ኢየሱስ ወያእምር
ከመ መኑ ውእቱ ወኢያበውሖ ሰብእ እስመ ሐጺር
በቆሙ ።
፬ ወሮፀ ቅድሜሁ ወዐርገ ዲበ ሰግላ ከመ ይርአዮ
እስመ እንተ ይእቲ ፍኖት ሀለዎ ይኅልፍ ።
፭ ወበጺሖ እግዚእ ኢየሱስ ህየ ነጸሮ ወይቤሎ ዘኬ
ዎስ አፍጥን ወረድ እስመ ዮም ሀለወኒ አበል ቤተከ ።
፮ ወአፍጠነ ወሪደ ወአግነዮ ኀበ ቤቱ እንዘ ይትፌ
ሣሕ ።
፯ ወርእዮሙ ኵሎሙ አንጐርጐሩ ወይቤሉ ኀበ ብእሲ
ኃጥእ ቦአ የዓል ።
፰ ወቆመ ዘኬዎስ ወይቤሎ ለእግዚእነ ናሁ እግዚኦየ
መንፈቀ ንዋይየ እሁብ ለነዳያን ወእመሂ በ ዘገፋዕ
ክዎ እፈድዮ ህየንተ አሐዱ ትርብዕተ ።

፱ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ዮምሰ ሕይወት ኮነ ለሰ
ብአ ዝንቱ ቤት እስመ አንተሂ ወልደ አብርሃም
አንተ ።

፲ እስመ መጽአ ወልደ እጓለ እመሕያው ይኅሥሥ
ወያድኅን ዘተኀጕለ ።

### ክፍል ፺ወ፮፣ ምሳሌ በእንተ እለ ነሥኡ ፲ተ ምናናተ ።

፲፩ ወእንዘ ይሰምዑ ዘንተ መሰለ ሎሙ እስመ ቅሩብ
ውእቱ ለኢየሩሳሌም ወይቤሎሙ ከመ ሶቤሃ ታስተ
ርኢ መንግሥተ እግዚአብሔር ።

## የሉቃስ ወንጌል ፲፱ ።

የናዝሬቱ ኢየሱስ ያልፋል አሉት ። ፴፯
ድምፁን ከፍ አድርጎ የዳዊት ልጅ ሆይ! ይቅር ፴፰
በለኝ አለ ።
የሚመሩትም ዝም ይል ዘንድ ተቈጡት ግን በጣም ፴፱
ጮኸ ብሎ የዳዊት ልጅ ማረኝ አለ ።
ጌታ ኢየሱስም ቆሞ ወደርሱ ያመጡት ዘንድ ፵
አዘዘ ።
ወደርሱም በቀረበ ጊዜ ምን ላደርግልህ ትወዳለህ? ፵፩
አለው፣ አቤቱ ዓይኖቼ እንዲያዩ ነው አለው ።
ጌታ ኢየሱስም እይ ሃይማኖትህ አዳነችህ አለው፣ ፵፪
ማቴ፡ ፱ ፳፪ ። ሉቃ፡ ፲፯ ፲፱ ።
ወዲያውም አየና ተከተለው፣ እግዚአብሔርንም ፵፫
አመሰገነው ሕዝቡም ሁሉ አይተው እግዚአብሔርን
አመሰገኑት፣ መዝ፡ ፻፫ ፱፣ መዝ ፻፫ ፩። ኢሳ፡ ፴፭ ፭።
ግ፡ ሐ፡ ፬ ፳፩ ። ፩ ጴጥ፡ ፪ ፱ ።

### ምዕራፍ ፲፱ ።

### ክፍል ፺፭፣ ስለ ቀራጩ ዘኬዎስ ።

ጌታ ኢየሱስም ወደ ኢያሪሆ ገብቶ ተመላለሰ ። ፩
እነሆም የቀራጮች አለቃ ስሙ ዘኬዎስ የተባለውን ፪
ሰው አገኘ፣ እሱም ባለጸጋ ነበር ።
ጌታ ኢየሱስም ያየው ዘንድና ማን እንደሆነ ያውቀ ፫
ዘንድ ይሻ ነበር፣ በቁመቱ አጭር ነበርና ሰው ይከ
ልለው ነበር ። ዮሐ፡ ፲፪ ፳፩ ።
ወደ ፊቱም ሮጦ ጌታ ኢየሱስን ያየው ዘንድ ከሾላ ፬
ላይ ወጣ፣ በዚያች መንገድ ያልፍ ዘንድ ነበረውና ።
ጌታ ኢየሱስም ከዚያ እንደ ደረሰ አየውና ዘኬዎስ ፭
ቶሎ ውረድ ዛሬ ከቤትህ እውላለሁና አለው ።
ፈጥኖም ወረደና ደስ እያለው ወደ ቤቱ ይዞት ገባ ። ፮

ሁሉም አይተው ከኃጢአተኛ ሰው ቤት ሊውል ገባ ፯
ብለው አንጐራጐሩ ። ምዕ፡ ፲፭ ፪ ። ማቴ፡ ፱ ፲፩ ።
ዘኬዎስም ቆመና ጌታችንን እንዲህ አለው፣ ጌታዬ! ፰
አሁን የገንዘቤን እኩሌታ ለነዳያን እሰጣለሁ የበደል
ኩትም ቢኖር በአንድ አራት እከፍላለሁ ። ዘፀ፡ ፳፪
፩-፱ ። ፩ ሳሙ፡ ፲፪ ፫ ።
ጌታ ኢየሱስም ዛሬስ ለዚህ ቤት ሰዎች ሕይወት ሆነ ፱
አንተም የአብርሃም ልጅ ነህና አለው ። ምዕ፡ ፲፫
፲፯ ። ገላት፡ ፫ ፯ ።
የሰው ልጅ የጠፋውን ሊፈልግና ሊያድን መጥ ፲
ቷልና ። ሕዝ፡ ፴፬ ፲፯ ። ማቴ፡ ፲፰ ፲፩ ። ፩ ጢሞ፡
፩ ፲፭ ።

### ክፍል ፺፮፣ ዐሥር ወቄት ስለ ተቀበሉት ሰዎች ምሳሌ ።

ይህንንም እየሰሙ መስለላቸው ወደ ኢየሩሳሌም ፲፩
ቀርቦ ስለ ነበር የእግዚአብሔር መንግሥት ወዲያ
ውኑ ትገለጥ መስሏቸው ነበርና ። ሉቃ ፲፯ ፣ ፳ ። ግብ
ሐዋ ፩ ፣ ፮ ።

፲፪ ወይቤ አሐዱ ብእሲ ክቡር ሖረ ብሔረ ርኁቀ ይን
ሣእ ሎቱ መንግሥተ ወይሠወጥ ።
፲፫ ወጸውዐ አግብርቲሁ ዐሥርተ ወወሀቦሙ ዐሥርተ
ምናናተ ወይቤሎሙ ተገበሩ እንከ እስከ አአቱ ።
፲፬ ወሰብአ ሀገሩሰ ይጸልእዎ ወፈነዉ ተናብልተ ድኅ
ሬሁ እንዘ ይብሉ ኢንፈቅድ ለዝንቱ ይንግሥ ላዕሌነ።
፲፭ ወእምዝ ሶበ አተወ ነሢኦ መንግሥተ አዘዘ ያምጽእ
ዎሙ ለአግብርቲሁ እለ ወሀቦሙ ወርቆ ከመ ያእ
ምር ዘከመ ተገበሩ ።
፲፮ ወመጽአ ቀዳማዊ ወይቤሎ እግዚኦ ምናንከ ዓሠርተ
ወዐሠርተ ምናናተ ረበኀኩ ።
፲፯ ወይቤሎ እግዚኡ አ ገብር ኄር ወምእመን ዘበው
ኁድ ምእመነ ኮንከ ዲበ ብዙኅ እሠይመከ፡ ተሠየም
ላዕለ ዐሠርቱ አህጉር ።
፲፰ ወመጽአ ካልኡሂ ወይቤሎ እግዚኦ ምናንከ ኃም
ስቱ፡ ወኃምስተ ምናናተ ረበኀኩ ።
፲፱ ወይቤሎ ሎቱኒ አንተኒ ተሠየም ላዕለ ኃምስቱ አህ
ጉር ።
፳ ወመጽአ ሣልሱኒ ወይቤሎ እግዚኦ ነዮ ምናንከ
እንተ ኀቤየ ጠብለልክዋ ወአንበርክዋ ውስተ ሰበንየ፤
፳፩ እስመ ፈራህኩከ እስመ አእምረከ ከመ ዕፁብ ብእሲ
አንተ ወትነሥእ ዘኢያንበርከ፡ ወተአርር ዘኢዘራ
እከ ወታስተጋብእ ዘኢዘረውከ ።
፳፪ ወይቤሎ እግዚኡ በከመ ቃልከ እኴንነከ አ ገብር
እኩይ ወሀካይ፡ ተአምረኒኑ ከመ ብእሲ ዕፁብ አነ
አነሥእ ዘኢያንበርኩ ወአአርር ዘኢዘራእኩ ወአስተ
ጋብእ ዘኢዘረውኩ ።
፳፫ ወለምንት ኢያግባእከ ወርቅየ ውስተ ማእድየ፡ ወለ
ልየ አነ አቲውየ እምአስተገበርክዎ ምስለ ረባኁ ።
፳፬ ወይቤሎሙ ለእለ ይቀውሙ ህየ ንሥኡ እምኔሁ
ዘንተ ምናነ ወሀብዎ ለዘቦቱ ዐሠርቱ ምናናት ።
፳፭ ወይቤልዎ እግዚኦ አኮኑ ቦቱ ዐሠርቱ ምናናት ።
፳፮ ወይቤሎሙ እብለክሙ ለኵሉ ዘቦ ይሁብዎ ወይዌስ
ክዎ፡ ወለዘሰ አልቦ እለሂ ቦ የኀይድዎ ።
፳፯ ወባሕቱ ለእልክቱሰ ጸላእትየ እለ ኢይፈቅዱ እን
ግሥ ላዕሌሆሙ አምጽእዎሙ ዝየ ወርግዝዎሙ
በቅድሜየ ።



እንዲህም አለ፡ አንድ የከበረ ሰው መንግሥት ይዞ ፲፪
ሊመለስ ወደ ሩቅ አገር ሄደ ። ማቴ ፳፭ ፡ ፲፬ ።
ዐሥር አገልጋዮቹን ጠርቶ፡ ዐሥር ምናን (ከረጢት ፲፫
ወርቅ) ሰጣቸውና ፡ እንግዲህ እስክመለስ ነግዱ አላ
ቸው ።
የሀገሩ ሰዎች ግን ይጠሉት ነበርና፡ ይህ በእኛ ላይ ፲፬
ሊነግሥብን አንፈቅድም ብለው እከታትለው መልእ
ክተኞችን ላኩ ። ዮሐ ፩ ፡ ፲፩ ።
ከዚህም ፀኋላ መንግሥትን ይዞ በተመለሰ ጊዜ፡ ፲፭
እንደ ነገዱ ያውቅ ዘንድ ወርቁን የሰጣቸውን አገል
ጋዮቹን እንዲያመጡአቸው አዘዘ ።
አንደኛው መጥቶ አቤቱ ገንዘብህ ዐሥር ነበር፡ ፲፮
አሥር ምናን አትርፌአለሁ አለው ።
ጌታውም በጥቂት የታመንክ ደግና ታማኝ አገልጋይ ፲፯
በብዙ ላይ እሾምሃለሁ በዐሥሩ አህጉር ላይ ተሾም
አለው ። ማቴ ፳፭ ፡ ፳፩ ። ምሳ ፲፯ ፡ ፲ ። ራእ ዮሐ
፪ ፡ ፳፯ - ፳፯ ።
ሁለተኛውም መጥቶ አቤቱ ምናንህ አምስት ነበር፡ ፲፰
እነሆ አምስት አትርፌአለሁ አለው ።
እሱንም፡ አንተም በአምስቱ አህጉር ተሾም አለው። ፲፱
ሦስተኛውም መጥቶ አቤቱ ጌታ ሆይ! ከኔ ዘንድ የነ ፳
በረችው ምናንህ እነኋት በመጠምጠሚያዬ ጠቅልዬ
አኑሬያት ነበር አለው ።
አንተ ያላኖርከውን የምትወስድ፡ ያልዘራኸውን የም ፳፩
ታጭድ፡ ያልበተንከውን የምትሰበስብ ጨካኝ እንደ
ሆንክ ስለ ሀወቅሁኸ ፈርቻሃለሁና ።
ጌታውም እንዲህ አለው አንተ ክፉና ሰነፍ ባርያ ፳፪
ያላኖርኩትን የምወስድ፡ ያልዘራሁትን የማጭድ፡
ያልበተንኩትን የምሰበስብ ጨካኝ ሰው እንደሆ
ንኩ ታውቀኛለኸን? እንግዲህ እንደ ቃልህ እፈ
ርድብሃለሁ ። ፪ ሳሙ ፩፡ ፲፯ ። ኢዮ ፲፭ ፡ ፮ ።
ማቴ ፲፪ ፡ ፴፯ ።
ለምን ወርቄን ወደ ግምጃ ቤት አልመለስከም? እኔ ፳፫
ራሴ ተመልሼ ከትርፉ ጋር ባሠራሁበት ነበር ።
ከዚያ የቆሙትንም ይህን ወርቅ ከእሱ ተቀብላችሁ ፳፬
አሥር ምናን ላለው ስጡት አላቸው ።
አቤቱ ዐሥር ምናን ያለው አይደለምን? አሉት ። ፳፭
እርሱም ላለው ሁሉ ይሰጡታል ይጨምሩለታል፡ ፳፮
ለሌለው ግን ያለውን ስንኳን ይወስዱበታል እላች
ኋለሁ አላቸው ። ምዕ ፰ ፡ ፲፰ ።
ነገር ግን እነዚያን ልነግሥባቸው የማይወዱ ጠላቶ ፳፯
ቼን ወደዚህ አምጡዋቸውና በፊቴ ውጉዋቸው ።

## ክፍል ፺ወ፯ ፡ በእንተ በአቱ ውስተ ኢየሩሳሌም ።

፳፰ ወዘንተ ብሂሎ አመልአ ቅድመ ወዐርገ ኢየሩሳሌም ።
፳፱ ወሶበ በጽሐ ቤተ ፋጌ ወቢታንያ ኀበ ደብር ዘስሙ
ኤሌዎን ፈነወ ክልኤተ እምአርዳኢሁ ።
፴ ወይቤሎሙ ሑሩ ሀገረ ዘቅድሜክሙ ወበዊአክሙ
ትረክቡ ዕዋለ እሥረ ዘኢተፅዕኖ ሰብእ ፍትሕዎ
ወአምጽእዎ ሊተ ።
፴፩ ወእመበ ዘይቤለክሙ ለምንት ትፈትሑ ፡ በሉ እግ
ዚኡ ይፈቅዶ ።
፴፪ ወሐዊሮሙ እለ ተፈነዉ ረከቡ በከመ ይቤሎሙ ።
፴፫ ወፈትሑ ዕዋለ ፡ ወእንዘ ይፈትሑ ዕዋለ ይቤልዎሙ
አጋእዝቲሁ ለምንት ትፈትሕዎ ለዕዋል ።
፴፬ ወይቤሉ እግዚኡ ይፈቅዶ ።
፴፭ ወነሥእዎ ወወሰድዎ ኀበ እግዚእ ኢየሱስ ወረሐኑ
አልባሲሆሙ ዲበ ዕዋል ወአጽዓንዎ ለእግዚእ ኢየ
ሱስ ዲቤሁ ።
፴፮ ወእንዘ የሐውር ነጸፉ አልባሲሆሙ ውስተ ፍኖት ።
፴፯ ወበጺሖሙ ኀበ ሙራደ ዐቀብ ዘደብረ ዘይት አኀዙ
ኵሎሙ አርዳኢሁ ይትፈሥሑ ወይሰብሕዎ ለእግዚ
አብሔር በዓቢይ ቃል በእንተ ኵሉ ኃይል ዘርእዩ ።
፴፰ እንዘ ይብሉ ቡሩክ ዘይመጽእ በስመ እግዚአብሔር
ወቡሩክ ንጉሠ እስራኤል ፡ ሰላም በምድር ወስብ
ሐት በአርያም ።
፴፱ ወበ እምፈሪሳውያን እለ ይቤልዎ በማእከለ ሕዝብ ፡
ሊቅ ገሥፆሙ ለአርዳኢከ ።
፵ ወአውሥአ ወይቤሎሙ እብለክሙ ለእመ አርመሙ
እሉ ፡ እሎንቱ አእባን ይኬልሑ ።
፵፩ ወበጺሖ ርእያ ለሀገር ወበከየ ላዕሌሃ ።
፵፪ ወይቤላ ሶበሰ ተአምሪ ዮም ሰላምኪ ወባሕቱ እም
ይእዜሰ ተሠወረ እምአዕይንትኪ ።
፵፫ ወይበጽሐኪ መዋዕል አመ የዓግቱኪ ፀርኪ ወይት
ዓየኑኪ ወየኀፅሩኪ ወያስተጋብኡኪ እምኵለሄ ።
፵፬ ወይነጽሑኪ ለኪ ወለውሉድኪ ምስሌኪ ወኢየኀ
ድጉ እብነ ዲበ እብን በውስቴትኪ እስመ ኢያእመ
ርኪ መዋዕለ ሣህልኪ ።



## ክፍል ፺፯ ፡ ወደ ኢየሩሳሌም ስለ መግባቱ ።

ይህንን ተናግሮ ጉዞውን ቀጥሎ ወደ ኢየሩሳሌም ፳፰
ወጣ ። ማር ፲ ፡ ፴፪ ።
ደብረ ዘይት ከሚባለው ተራራ አጠገብ ወደ ቤተ ፳፱
ፋጌና ወደ ቢታንያ በደረሰ ጊዜ ከደቀ መዛሙርቱ
ሁለቱን ላከ ። ዘካ ፲፬ ፡ ፬ ። ማቴ ፳፩ ፡ ፩ - ፱ ። ዮሐ
፲፪ ፡ ፲፪ - ፲፮ ።
እንዲህም አላቸው ፡ በፊታችሁ ወደ አለችው አገር ፴
ሂዱ ፡ ገብታችሁም ሰው ያልተቀመጠበት የታሠረ
ውርንጫ ታገኛላችሁ ፡ ፈትታችሁ አምጡልኝ ።
ማር ፲፩ ፡ ፪ ።
ለምን ትፈቱታላችሁ የሚላችሁ ቢኖር ጌታው ይሻ ፴፩
ዋል በሉ ። መዝ ፶ ፡ ፲ ።
የተላኩትም ሂደው እንደ አላቸው አገኙ ። ፴፪
ውርንጫውን ፈቱ ፡ ውርንጫውንም ሲፈቱ ባለቤ ፴፫
ቶቹ ግልገሉን ለምን ትፈቱታላችሁ? አሏቸው ።
ጌታው ይሻዋል አሉ ። ዮሐ ፲፪ ፡ ፲፬ ። ፴፬
ይዘውም ወደ ጌታ ኢየሱስ ወሰዱትና በግልገሉ ፴፭
ላይ ልብሳቸውን ጐዝጉዘው ጌታ ኢየሱስን በዚያ
ላይ አስቀመጡት ። ፪ ነገ ፱ ፡ ፲፫ ።
ሲሄድም በመንገድ ልብሶቻቸውን አነጠፉ ። ፴፮
ወደ ደብረ ዘይት ዐቀበት መውረጃም በደረሱ ጊዜ ፴፯
ደቀ መዛሙርቱ በሙሉ ስለ አዩት ኀይል ሁሉ ደስ
ብሎአቸው እግዚአብሔርን በታላቅ ቃል ሊያመሰ
ግኑት ጀመሩ ።
በእግዚአብሔር ስም የሚመጣ የተባረከ ነው ፡ የእስ ፴፰
ራኤል ንጉሥ የተባረከ ነው ፡ በምድር ሰላም ፡ በአር
ያም ምስጋና ይሁን እያሉ ። መዝ ፻፲፰ ፡ ፳፮ ። ፩ ጢሞ
፩ ፡ ፲፯ ። ምዕ ፪ ፡ ፲፬ ።
ከፈሪሳውያን ሰዎችም በሕዝቡ መካከል መምህር ! ፴፱
ደቀ መዛሙርትህን ገሥፃቸው የሚሉት ነበሩ ።
እርሱም እነዚህ ዝም ቢሉ ፡ እሊህ ድንጋዮች ይናገ ፵
ራሉ ብሎ መለሰላቸው ። ዕንባ ፪ ፡ ፲፩ ። ፪ ጴጥ ፪ ፡ ፲፮ ።
በደረሰ ጊዜም አገሪቱን አይቶ አለቀሰላት ። ፪ ነገ ፰ ፡ ፵፩
፲፩ ። ኢሳ ፶፫ ፫ ። ሆሴ ፲፩ ፡ ፰ ። ዮሐ ፲፩ ፡ ፴፭ ።
እንዲህም አላት ብታውቂስ ሰላምሽ ዛሬ ነበረ ፡ ፵፪
ከእንግዲህ ወዲህ ግን ከዓይኖችሽ ተሠውሯል ።
ዘዳ ፴፪ ፡ ፳፱ ። ኢሳ ፶፱ ፡ ፰ ።
ጠላቶችሽ አንቺን የሚከቡበት ቀን ይመጣል ፡ ይከ ፵፫
ትሙብሻል ፡ ይከቡሻል ፡ በአራቱ መዓዝን ያስጨን
ቁሻል ። ኢሳ ፳፱ ፡ ፫ ። ኤር ፮ ፡ ፫ - ፮ ። ሕዝ ፳፩ ፡ ፳፪ ።
ይጥሉሻል ፡ ልጆችሽንም ከንቺ ጋር ይጥሏቸዋል ፡ ፵፬
ደንጊያ በደንጊያ ላይ አይተዉልሽም ፡ የይቅርታሽን
ቀን አላወቅሽምና ። ፩ ነገ ፱ ፡ ፯ ። ማቴ ፳፬ ፡ ፪ ።
ሚክ ፫ ።

ክፍል ፺ወ፰ ፡ በእንተ ዘከመ ሰደዶሙ ለእለ ይሠይጡ ወይሣየጡ በቤተ መቅደስ ።

፵፭ ወቦአ ምኵራበ ወሰደደ ኵሎሙ እለ ይሠይጡ ወይ
ሣየጡ በቤተ መቅደስ ፡ ወገፍትዐ ማእዳቲሆሙ ለመ
ወልጣን ወመናብርቲሆሙ ለእለ ይሠይጡ ርግበ ።

፵፮ ወይቤሎሙ ጽሑፍ ዘይብል ቤትየሰ ቤተ ጸሎት
ይሰመይ ፡ ወአንትሙሰ ረሰይክምዎ በአተ ፈያት
ወሰረቅት ።
፵፯ ወኵሎ አሚረ ይሜህሮሙ በምኵራብ ወየኃሥሡ
ሊቃነ ካህናት ወጸሐፍት ወሊቃናተ ሕዝብ በዘይቀ
ትልዎ ።
፵፰ ወኃጥኡ ዘይሬስይዎ እስመ ኵሎሙ ሕዝብ ይሰ
ቀሉ በአሰምአቱ ።

ምዕራፍ ፳ ።

ክፍል ፺ወ፱ ፡ በእንተ ዘከመ ተስእልዎ ሊቃነ ካህናት ።

፩ ወእምዝ አሐተ ዕለተ እንዘ ይሜህሮሙ ለሕዝብ
በምኵራብ ወይነግሮሙ ቆሙ ላዕሌሁ ሊቃነ ካህናት
ወጸሐፍት ወረበናት ።

፪ ወይቤልዎ ንግረነ በመባሕተ መኑ ትገብር ዘንተ ፡
ወመኑ አብሐከ ትግበር ከመዝ ።

፫ ወአውሥአ ወይቤሎሙ እሴአለክሙ አነሂ አሐተ
ነገረ ወንግሩኒ ።
፬ ጥምቀቱ ለዮሐንስ እምአይቴ ይእቲ ፡ እምሰማይኑ
ወሚመ እምሰብእ ።
፭ ወተባሀሉ በበይናቲሆሙ እመሂ ንብሎ እምሰማይ
ይብለነ እፎ ኢአመንክምዎ ።
፮ ወእመሂ ንብሎ እምሰብእ ይዌግሩነ ኵሉ ሕዝብ
እስመ ኵሎሙ ተአመንዎ ለዮሐንስ ከመ ነቢይ
ውእቱ ።
፯ ወአውሥእዎ ወይቤልዎ ኢነአምር እምኀበ ኮነ ።

፰ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አነሂ ኢይነግረክሙ
በመባሕተ መኑ እገብር ከመዝ ።

ክፍል ፻ ፡ በእንተ ዐቀብተ ወይን ።

፱ ወአኀዘ ይመስል ሎሙ ለሕዝብ ዘንተ ምሳሌ ወይቤ
ሎሙ ብእሲ ተከለ ወይነ ወሚመ ሎቱ ዐቀብተ ለወ
ይኑ ወአክረየ ምክያደ ወሐነፀ ማኅፈደ ወነገደ ርኁቀ
ብሔረ ወጐንደየ አቲወ ።

፲ ወአመ ኮነ ጊዜ ፍሬሁ ፈነወ ገብሮ ኀበ ዐቀብተ

ክፍል ፺፰ ፡ በቤተ መቅደስ የሚገዙትንና የሚሸጡትን ስለ ማባረሩ ።

ወደ ምኵራብም ገብቶ በቤተ መቅደስ የሚሸጡት ፵፭
ንና የሚገዙትን ሁሉ አስወጣ ፡ የለዋጮችንም
ሰደቃ የርግብ ሻጮችንም ወንበር ገለበጠ ። ማር
፲፩ ፡ ፲፭ - ፲፰ ። ዮሐ ፪ ፡ ፲፫ - ፲፯ ።
ቤቴ የጸሎት ቤት ይባላል የሚል ጽሑፍ አለ ፡ ፵፮
እናንተ ግን ፡ የሌባና ፡ የቀማኛ ዋሻ አደረጋችሁት
አላቸው ። መዝ ፷፫ ፡ ፭ ። ኢሳ ፶፮ ፡ ፯ ። ኤር ፯ ፡ ፲፩ ።
ዘወትር በምኵራብ ያስተምራቸው ነበር ፡ የካህናት ፵፯
አለቆች ፡ ጻፎችና የሕዝብ ታላላቆችም ሊገድሉት
ይሹ ነበር ።
ግን የሚያደርጉትን አጡ ፡ ሕዝቡ ሁሉ በትምህርቱ ፵፰
ይመሰጡ ነበርና ።

ምዕራፍ ፳ ፤

ክፍል ፺፱ ፡ የካህናት አለቆች እንደ ጠየቁት ።

ከዚህም በኋላ አንድ ቀን ሕዝቡን በምኵራብ ሲያስ ፩
ተምራቸውና ሲነግራቸው ፡ የካህናት አለቆች ፡ ጻፎ
ችና ሽማግሌዎች ተነሡበት ። ማቴ ፳፩ ፡ ፳፫ - ፳፯ ።
ማር ፲፩ ፡ ፳፯ - ፴፫ ።
ይህን በማን ሥልጣን እንደምትሠራ ንገረን ፡ ይህን ፪
ንስ እንድታደርግ ማን ፈቀደልህ ? አሉት ። ግብ
ሐዋ ፬ ፡ ፯ ።
እሱም መልሶ እንዲህ አላቸው እኔም አንዲት ነገር ፫
እጠይቃችኋለሁ ንገሩኝ ።
የዮሐንስ ጥምቀት ከወዴት ናት ፡ ከሰማይ ? ወይስ ፬
ከሰው ? ።
እርስ በርሳቸውም እንዲህ ተባባሉ ፡ ከሰማይ ነው ፭
ብንለው ለምን አላመናችሁት ? ይለናል ።
ከሰው ነው ብንለውም ሕዝቡ ሁሉ ይወግሩናል ፡ ፮
ሁሉም ዮሐንስ ነቢይ እንደሆነ አምነዉበታልና ።
ማቴ ፲፬ ፡ ፭ ። ምዕ ፯ ፡ ፳፱ ።
ከወዴት እንደሆነች አናውቅም ብለው መለሱለት ። ፯
ኢዮ ፳፬ ፡ ፲፫ ። ሮሜ ፲፰ ፡ ፳፩ ።
ጌታ ኢየሱስም ፡ እኔም ይህንን በማን ሥልጣን እንዳ ፰
ደርግ አልነግራችሁም አላቸው ። ኢዮ ፭ ፡ ፲፪ - ፲፫ ።

ክፍል ፻ ፡ ስለ ወይን ጠባቆች ።

ለሕዝቡም ይህን ምሳሌ ይመስልላቸው ጀመር እን ፱
ዲህም አላቸው ፤ አንድ ሰው ወይን ተከለና ለወይኑ
ጠባቆች ሾመለት መጥመቂያ አስቆፈረ ግንብም
ሠራና ወደ ሩቅ አገር ሄዶ ሳይመለስ ዘገየ ። መዝ፡
፹ ፱ ። ኢሳ፡ ፭ ፩ ። ኤር፡ ፪ ፳፩ ።
የመከር ወራት በሆነ ጊዜም ወደ ወይኑ ጠባቂዎች ፲

ወይን ከመ ይፈንዉ ሎቱ እምፍሬ ወይኑ ወዘበጥዎ
ዐቀብተ ወይን ለገብሩ ወፈነውዎ ዕራቆ ።

፲፩ ወዳግመ ፈነወ ካልአነ ገብሮ ፡ ወኪያሁኒ ዘበጥዎ
ወአኅሠርዎ ወፈነውዎ ዕራቆ ።
፲፪ ወካዕበ ፈነወ ሣልሰኒ ገብሮ ፡ ወኪያሁኒ ፈቀዕዎ
ወሰደድዎ ።
፲፫ ወይቤ በዐለ ዓፀደ ወይን ምንተ እንከ እሬሲ እፌኑ
ወልድየ ዘአፈቅር ለእመ ኪያሁ የኀፍሩ ርእዮሙ
ወፈነዎ ።

፲፬ ወሶበ ርእይዎ ዐቀብተ ወይን ተማከሩ ወይቤሉ
ዝንቱ ውእቱ ወራሲሁ ንዑ ንቅትሎ ወንርከብ ርስቶ ፤

፲፭ ወአውፅእዎ እፍአ እምዓፀደ ወይን ወቀተልዎ ።

፲፮ ወሶበ መጽአ በዐለ ዓፀደ ወይን ምንተ እንከ ይሬስ
ዮሙ ይመጽእ ወይቀትሎሙ ለእልክቱ ዐቀብተ
ዓፀደ ወይን ወይሁብ ወይኖ ለካልአን ዐቀብት ፡ ወሰ
ሚዖሙ ቃሎ ይቤሉ ሐሰ ኢይከውን ከመዝ ።

፲፯ ወነጸሮሙ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ ምንትኑመ
ጽሑፍ ዘይብል እብን እንተ መነንዋ ነደቅት ይእቲ
ከነት ውስተ ርእሰ ማዕዘንት ።

፲፰ ወኵሉ ዘወድቀ ዲበ ይእቲ እብን ይትቀጠቀጥ ወለ
ዘኒ ወድቀት ላዕሌሁ ትቀጠቅጦ ።

፲፱ ወፈቀዱ ሊቃነ ካህናት ወጸሐፍት የአኀዝዎ ሶቤሃ
ወፈርህዎሙ ለሕዝብ እስመ አእመሩ ከመ በእንቲ
አሆሙ መሰለ ከመዝ ።

ክፍል ፪ወ፩ ፡ በእንተ ውሂበ ጸባሕት ለቄሣር ።

፳ ወተግኒሦሙ እምኔሁ አጽንሑ ሎቱ እለ ይትዐቀ
ብዎ ወፈነዉ ኀቤሁ ሰብአ ዐይን እለ ያጸድቁ ርእ
ሰሙ ከመ ያስሕትዎ በቃሉ ወከመ ያግብእዎ ለመኳ
ንንት ወለመሳፍንት ።
፳፩ ወተስእልዎ ወይቤልዎ ሊቅ ነአምር ከመ ጽድቀ
ትነግር ወትሜህር ወኢታደሉ ለገጽ ወኢለመኑሂ
ወርቱዐ ትሜህር ፍኖተ እግዚአብሔር ።

፳፪ ይከውነነሁ ነሀብ ጸባሕተ ለቄሣር ወሚመ አልበ ።

፳፫ ወአእመሮሙ ትምይንቶሙ ወይቤሎሙ ለምንት
ታሜክሩኒ አርእዩኒ ዲናረ ።

የሉቃስ ወንጌል ፳ ።

አገልጋዩን ላከ ከወይኑ ፍሬ ይልኩለት ዘንድ ፡ የወይ
ኑን ጠባቂዎች ግን አገልጋዩን ደብድበው ባዶ እጁ
ንም ሰደዱት ። ፪ ነገ፡ ፲፯ ፲፫ - ፲፬ ። ፪ ዜና መዋ፡
፴፯ ፲፭ - ፲፯ ።
ዳግመኛም ሌላው አገልጋዩን ላከ እሱንም ደብድ ፲፩
በው አዋርደው ባዶ እጁን ሰደዱት ።
ደግሞ ሦስተኛ አገልጋዩን ላከ እሱንም አቊስለው ፲፪
ሰደዱት ። ነህ፡ ፱ ፳፱ - ፴ ።
የወይኑ ባለቤትም እንግዲህ ምን ላድርግ? ምናል ፲፫
ባት እሱን እንኳ አይተው ያፍሩት እንደሆን ልጄን
ልላከው ብሎ ላከው ። ኢሳ፡ ፯ ፲፬ ። ዮሐ፡ ፫ ፲፯ ።
ሮሜ ፰ ፫ ። ገላ፡ ፬ ፬ ።
የወይን ጠባቂዎችም ባዩት ጊዜ ወራሹ ይህ ነው ኑ ፲፬
እንግደለውና ርስቱን እንውሰድ አሉ ። መዝ፡ ፪ ፰
ኢሳ፡ ፱ ፯ ። ዕብ፡ ፩ ፪ ።
ከወይኑ ቦታም ወደ ውጭ አውጥተው ገደሉት ። ፲፭
ግብረ ሐ፡ ፫ ፲፭ ። ፩ ቆሮ፡ ፪ ፰ ።
የወይኑ ባለቤት በመጣ ጊዜ እንግዲህ ምን ያደርጋ ፲፮
ቸዋል? መጥቶ እነዚያን የወይን ቦታ ጠባቂዎች
ይገድላቸዋል ወይኑንም ለሌሎች ጠባቂዎች ይሰ
ጣል ፤ ቃሉንም ሰምተው አይሆንም እንዲህ አይደ
ረግም አሉ ።
ጌታ ኢየሱስም አያቸውና እንዲህ አላቸው ፡ አና ፲፯
ጢዎች የናቁት ደንጊያ በመዓዝን ራስ ላይ ሆነች
የሚለው ጽሑፍ ምንድነው? መዝ፡ ፻፲፰ ፳፪ ።
ኢሳ፡ ፰ ፲፬ ፤ ፩ ጴጥ ፡ ፪ ፡ ፯ ።
በዚያች ደንጊያ ላይ የወደቀ ሁሉ ይቀጠቀጣል የወ ፲፰
ደቀችበትንም ትቀጠቅጠዋለች ። ኢሳ ፡ ፰ ፲፭ ።
ዳን ፡ ፪ ፴፬ - ፴፭ ። ሮሜ ፱ ፴፫ ። ፩ ጴጥ ፡ ፪ ፯ ።
ያን ጊዜ የካህናት አለቆችና ጸፎች ሊይዙት ወደዱ ፲፱
ግን ሕዝቡን ፈሯቸው ይህንን ስለ እነሱ እንደ መሰለ
አውቀዋልና ። ምዕ፡ ፲፱ ፵፰ ።

ክፍል ፪፩ ፡ ለቄሣር ግብር ስለ መስጠት ።

ከእነሱም ሂደው የሚጠባበቁትን አዘጋጁለት በቃሉ ፳
ያስቱት ወደ መኳንንት ወደ መሳፍንትም ሊያከስ
ሱት ራሳቸውን የሚያመጻድቁ ጐብኝዎችን ወደ
እሱ ሰደዱ ። ማቴ፡ ፳፪ ፲፭-፳፪። ማር፡ ፲፪ ፲፫-፲፯ ።
እነሱም እንዲህ ብለው ጠየቁት ፤ መምህር ፡ አንተ ፳፩
እውነት እንደምትናገርና እንደምታስተምር ለማንም
ለማን ፊት አይተህ እንደማታዳላ የእግዚአብሔርንም
መንገድ በቀጥታ እንደምታስተምር እናውቃለን።
ማር፡ ፲፪ ፲፬ ።
ለቄሣር ግብር መስጠት ይገባናል ? ወይስ አይገ ፳፪
ባንም?
ተንኰላቸውንም አውቆ ለምን ትፈትኑኛላችሁ? ፳፫
ወርቁን አሳዩኝ አላቸው ።

፳፬ ወአምጽኡ ወአርአይዎ ፡ ወይቤሎሙ ዘመኑ መል ክዑ ወመጽሐፉ ወአውሥእዎ ወይቤልዎ ዘቄሣር ።

አምጥተው አሳዩት መልኩ ጽሕፈቱስ የማነው? አላቸው ፤ የቄሣር ነው ብለው መለሱለት ። ፳፬

፳፭ ወይቤሎሙ ሀቡ ዘቄሣር ለቄሣር ፡ ወዘእግዚአብሔር ለእግዚአብሔር ።

እንኪያስ የቄሣርን ለቄሣር፡ የእግዚአብሔርንም ለእግ ዚአብሔር ስጡ አላቸው ። ፳፭

፳፮ ወስእንዎ አስሕቶቶ በቃሉ በቅድመ ኵሉ ሕዝብ ወአንከሩ ሣዕሣዐ አፉሁ ወአውሥአቶ ወአርመሙ ።

በሕዝቡ ሁሉ ፊት በአነጋገሩ ማሳት ተሳናቸው አክናውኖ መናገሩንና መልሱን አድንቀው ዝም አሉ። ፳፮

## ክፍል ፲ወ፱ ፡ በእንተ እለ ይብሉ አልቦ ትንሣኤ ሙታን ።

## ክፍል ፲፱ ፡ ትንሣኤ ሙታን የለም ስለሚሉ ሰዎች ።

፳፯ ወመጽኡ ኀቤሁ ሰዱቃውያን እለ ይብሉ ኢየሐ ይዉ ምዉታን ።

ሙታን አይነሡም የሚሉ ሰዱቃውያንም ወደ እሱ መጡ ። ማቴ፡ ፳፪ ፳፫ - ፴፫ ። ማር፡ ፲፪ ፲፰-፳፯ ። ግብ ሐዋ ፬ ፩ - ፪ ። ፳፯

፳፰ ወተስእልዎ ወይቤልዎ ሊቅ ሙሴ ጸሐፈ ለነ እንዘ ይብል ፡ ለእመበ ብእሲ ዘሞተ እኁሁ ወኀደገ ብእሲቶ እንዘ አልቦ ውሉድ ያውስባ እኁሁ ለብእሲቱ ወያ ቅም ዘርአ ለእኁሁ ።

እንዲህ ብለው ጠየቁት ፤ መምህር ሙሴ "ወንድሙ ልጅ ሳይወልድ ሚስቱን ትቶ የሞተበት ሰው ቢኖር ወንድሙ ሚስቱን አግብቶ ለወንድሙ ዘር ይተካ" ሲል ጽፎልናል ። ዘፍ፡ ፴፰ ፰ ። ዘዳ፡ ፳፭ ፭ ። ፳፰

፳፱ ወሀለዉ እንከ ኀቤነ ሰብዓቱ አኀው ወአውሰበ ዘይ ልኅቅ ብእሲተ ወሞተ እንዘ አልቦ ውሉድ ።

እንግዲህ ከእኛ ዘንድ ሰባት ወንድማማች ነበሩ ታላቁ ሚስት አግብቶ ልጅ ሳይወልድ ሞተ ። ፳፱

፴ ወከማሁ አውሰበ ካልኡኒ ወሣልሱኒ ነሥአ ከማሁ ወኢኀደጉ ውሉደ ።

ሁለተኛው አገባት ሦስተኛውም እንዲሁ አገባት ልጅም አልተዉም ። ፴

፴፩ ወሰብዐቲሆሙ ከማሁ አውሰብዋ ወሞቱ እንዘ አል ቦሙ ውሉድ ።

ሰባቱም እንዲሁ በመከታተል አግብተዋት ልጅ ሳይወልዱ ሞቱ ። ፴፩

፴፪ ወድኅረ ኵሎሙ ሞተት ይእቲ ብእሲት ።

ከሁሉም በኋላ ያቺ ሴት ሞተች ። ፴፪

፴፫ ወአመ የሐይዉ እንከ ምዉታን ለመኑ እምኔሆሙ ትከውኖ ብእሲተ እስመ ናሁ ሰብዐቲሆሙ አው ሰብዋ ።

እንግዲህ ሙታን በተነሡ ጊዜ ከነሱ ለማንኛው ሚስት ትሆነዋለች እነሆ ሰባቱ ሁሉ አግብተዋታልና። ፴፫

፴፬ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ ውሉደ ዝንቱ ዓለም ያወስቡ ወይትዋሰቡ ወይወልዱ ወይት ዋለዱ ።

ጌታ ኢየሱስም መልሶ እንዲህ አላቸው ፤ የዚህ ዓለም ልጆች ያገባሉ ይጋባሉ ይወልዳሉ ይዋለዳሉ ። ፴፬

፴፭ ወእለሰ ይደልዎሙ ይርከብዎ ለዝክቱ ዓለም አመ የሐይዉ ሙታን ኢያወስቡ ወኢይትዋሰቡ ።

ሙታን በሚነሡበት ጊዜ ያን ዓለም ሊወርሱት የሚገባቸውን ግን አያገቡም አይጋቡም ። ፩ ቆሮ፡ ፲፭ ፳፫ - ፶፫ ። ፴፭

፴፮ ወኢይትከሀሎሙ እንከ መዊተ እላ ከመ መላእክተ እግዚአብሔር እሙንቱ ወውሉደ እግዚአብሔር ይከውኑ ወውሉደ ሕይወት እሙንቱ ።

ከእንግዲህ ወዲህ ሞት የለባቸውም እንደ እግዚአብ ሔር መላእክት ናቸው ፤ የእግዚአብሔር ልጆች ይሆ ናሉ የሕይወት ልጆችም ናቸው እንጂ ። ፩ ቆሮ፡ ፲፭ ፵፪ - ፶፪ ። ሮሜ ፰ ፳፫ ። ፩ ዮሐ፡ ፫ ፪። ፴፮

፴፯ ወከመሰ የሐይዉ ሙታን ሙሴሂ ነገረ ዘከመ ይቤሎ እግዚአብሔር በኀበ ዕፀ ጳጦስ አነ ውእቱ አምላከ አብርሃም ፡ ወአምላከ ይስሐቅ ፡ ወአምላከ ያዕቆብ ።

ሙታን እንደሚነሡስ እግዚአብሔር በቍጥቋጦ ሆኖ እኔ የአብርሃም አምላክ ፤ የይስሐቅ አምላክ ፤ የያዕቆብ አምላክ ነኝ እንዳለው ሙሴም ተናግሯል ። ዘፀአ ፫ ፡ ፮ ። ግብ ሐዋ ፯ ፡ ፴፪ ። ፴፯

፴፰ ኢኮነኬ አምላከ ሙታን አላ አምላከ ሕያዋን ውእቱ እስመ ኵሎሙ ሕያዋን እሙንቱ በኀቤሁ ።

እንኪያስ የሕያዋን አምላክ እንጂ የሙታን አምላክ አይደለም ሁሉም በእርሱ ዘንድ ሕያዋን ናቸውና ። መዝ ፲፮ ፡ ፭ - ፲፩ ። ሮሜ ፬ ፡ ፲፯ ። ቈላስ ፫ ፡ ፫ - ፬ ። ዕብ ፲፩ ፡ ፲፮ ። ፴፰

፴፱ ወአውሥኡ ሰብአ እምጸሐፍት ወይቤሉ ሊቅ ሠናየ ትቤ ።

ከጻፎችም ወገን የሆኑ ሰዎች መምህር ፤ መልካም ብለሃል ብለው መለሱ ። ፴፱

፵ ወአልቦ እንከ መኑሂ ዘተኀበለ ይሰአሎ ።

ከዚያ ወዲያ ግን ማንም ሊጠይቀው የደፈረ የለም ። ፵

### ክፍል ፲ወ፫ ፡ ዘከመ ተስእሎሙ እግዚእነ ለፈሪሳውያን ።

፵፩ ወይቤሎሙ እፎ ይብልዎ ለክርስቶስ ወልደ ዳዊት ።

፵፪ ወለሊሁ ዳዊት ይቤ በመጽሐፈ መዝሙር ይቤሎ እግዚእ ለእግዚእየ ንበር በየማንየ ።

፵፫ እስከ አገብእሙ ለጸላእትከ ታሕተ መከየደ እገሪከ ።

፵፬ ዘለሊሁ እንከ ዳዊት እግዚእየ ይቤሎ እፎ እንከ ይከውኖ ወልዶ ።

፵፭ ወእንዘ ኵሎሙ ሕዝብ ይሰምዑ ይቤሎሙ ለአርዳኢሁ ።

፵፮ ተዐቀብዎሙ ለጸሐፍት እለ ይፈቅዱ ያንሶስዉ ተላቢሶሙ ወያፈቅሩ ተአምኆ በምሥያጣት ፡ ወንቢረ ፍጽም በውስተ አዕዋዳት ወርእሰ ምርፋቃት በውስተ ምሳሓት ።

፵፯ እለ ይውኅጥዎን ለአብያተ መበለታት ወበምክንያት ያነውኁ ጸሎተ ፡ እሙንቱ ይነሥኡ ዘየዐቢ ኵነኔ ።

### ምዕራፍ ፳ወ፩ ፡
### ክፍል ፲ወ፬ በእንተ ጸሪቀ መበለት ።

፩ ወነጸረ ወርእየ አብዕልተ ዘያበውኡ መባአሙ ውስተ ሙዳየ ምጽዋት ።

፪ ወርእየ ዕቤረ መበለተ እንዘ ታበውእ ክልኤ ጸራይቀ ።

፫ ወይቤሎሙ አማን እብለክሙ ከመ ዛቲ ዕቤር ነዳይት አብዝኀት አብአ መባአ ለእግዚአብሔር ።

፬ እስመ እሉ ኵሎሙ እምተረፎሙ አብኡ መባአ ለእግዚአብሔር ፡ ወዛቲሰ እምተጽናሳ ኵሎ ጥሪታ ዘበ አብአት ።

### ክፍል ፲ወ፭ ፡ በእንተ ምዝባሬ ቤተ መቅደስ ወኢየሩሳሌም ።

፭ ወበ እለ ይቤልዎ በእንተ ቤተ መቅደስ ሠናይ አበኒሁ ወሥርገው ንድቁ ።

፮ ወይቤሎሙ ትሬእዩኑ ዘንተ ፤ ይመጽእ መዋዕል አመ ኢይትኀደግ ዝየ እብን ዲበ እብን ዘኢይትነሠት ።

፯ ወተስእልዎ ወይቤልዎ ሊቀ ማእዚ ይከውን ዝንቱ ወምንት ተአምሪሁ አመ ይከውን ዝንቱ ።

፰ ወይቤሎሙ ዑቁ ኢያስሕቱክሙ ብዙኃን ይመጽኡ



### ክፍል ፲፫፡ ጌታችን ፈሪሳውያንን እንደ ጠየቃቸው ።

ክርስቶስን እንዴት የዳዊት ልጅ ይሉታል? አላ ፵፩
ቸው ። ኢሳ ፱ ፡ ፮ - ፯ ። ማቴ ፳፪ ፡ ፵፩ - ፵፭ ። ማር
፲፪ ፡ ፴፭ ።
እሱ ዳዊት በመዝሙር መጽሐፍ እንዲህ ብሏል ፵፪
"ጌታ ጌታዬን በቀኜ ተቀመጥ" አለው ። መዝ ፻፲ ፡
፩ ። ግብ ሐዋ ፪ ፡ ፴፬ ። ፩ ቆሮ ፲፭ ፡ ፳፭ ።
ጠላቶችህን ከእግርህ ጫማ በታች እስከደርጋቸው ፵፫
ድረስ ።
እንግዲህ እሱ ራሱ ዳዊት ጌታዬ ያለው እንዴት ፵፬
ልጁ ይሆናል? ።
ሕዝቡም ሁሉ እየሰሙ ደቀ መዛሙርቱን እንዲህ ፵፭
አላቸው ።
ልብሳቸውን እንዘርፍፈው ወዲያ ወዲህ ማለትን ፵፮
የሚሹ በገበያ እጅ መንሣትን፥ በአደባባይ ፊት ለፊት
መቀመጥን፤ በማእድ ጊዜ በራስጌ መቀመጥን የሚ
ወዱ ጻፎችን ዕወቁባቸው ። ምዕ ፲፩ ፡ ፵፫ ። ማቴ
፳፫ ፡ ፮ ።
የመበለቶችን (የድኾችን) ገንዘብ የሚበሉ ለምክንያ ፵፯
ትም ጸሎትን የሚያስረዝሙ፥ እነዚህ ከፍተኛ ቅጣ
ትን ይቀበላሉ ። ማር ፲፪ ፡ ፵ ።

### ምዕራፍ ፳፩፤
### ክፍል ፲፬፡ ስለ ድኻይቱ መኃልቅ ።

በሙዳየ ምጽዋቱ መባቸውን የሚያገቡ ባለ ጸጎችን ፩
አየ ተመለከተ ። ፪ ነገ ፲፪ ፡ ፱ ። ማር ፡ ፲፪ ፡ ፵፩ - ፵፪ ።
አንዲት ድኻ ባልቴት ሁለት መኃልቅ ስታገባ አየ ። ፪

እንዲህም አላቸው ይህቺ ድኻ ባልቴት ለእግዚአብ ፫
ሔር ብዙ መባ እንዳገባች በእውነት እነግራችኋለሁ ።
፪ ቆሮ ፰ ፡ ፲፪ ።
እነዚህ ሁሉ ከተረፋቸው ለእግዚአብሔር መባ ሰጥ ፬
ተዋልና፤ ያቺ ግን ከድኽነቷ ያላት ጥሪቷን ሁሉ
አገባች ።

### ክፍል ፲፭፡ ስለ ኢየሩሳሌም መፈታትና ስለ ቤተ መቅደስ መፍረስ ።

ስለ ቤተ መቅደስም ደንጊያው ያማረ ነው፥ አሠራ ፭
ሩም ያጌጠ ነው ያሉት ነበሩ ። ማቴ ፳፬ ፡ ፩ - ፳፬ ።
እንዲህም አላቸው ይህን ታያላችሁን? ደንጊያ በደን ፮
ጊያ ላይ ሳይፈርስ የማይቀርበት ጊዜ ይመጣል ።
ምዕ ፲፱ ፡ ፵፬ ፡ ሚክ ፫ ፡ ፲፪ ።
እነሱም መምህር! ይህ መቼ ይደረጋል? በሚሆን ፯
በትስ ጊዜ ምልክቱ ምንድነው? ብለው ጠየቁት ።
እርሱም እንዲህ አላቸው፥ ብዙዎች እኔ ክርስቶስ ፰

በስምየ እንዘ ይብሉ አነ ውእቱ ክርስቶስ ወበጽሐ
ዕድሜሁ ወኢትሖሩ ወኢትትልውዎሙ ።

፱ ወአመ ሰማዕክሙ ቀትለ ወሀከከ ኢትደንግፁ እስመ
ይከውን ቅድመ ከመዝ ወበሕቱ አኮ ሶቤሃ ዘየኃልቅ ።

፲ ወይትነሥኡ ሕዝብ ዲበ ሕዝብ ወንግሥት ዲበ
ንግሥት ።

፲፩ ወይመጽእ ዓቢይ ድልቅልቅ ወረኃብ በበብሔሩ
ወፍርሀት ላዕለ ሰብእ ወተአምር ዓቢይ ይከውን
እምሰማይ ።

፲፪ ወእምቅድመ ዝንቱ ኵሉ ይእኅዙክሙ ወይወስዱ
ክሙ አዕዋዳተ ወይሰድዱክሙ ወይሞቅሑክሙ ወይ
ወስዱክሙ ኀበ ነገሥት ወመሳፍንት በእንተ ስምየ ።

፲፫ ወዝንቱ ይረክበክሙ ከመ ይኩን ስምዐ ላዕሌሆሙ ።

፲፬ ዑቁ ኢተሐልዩ በልብክሙ ዘትብሉ ።

፲፭ አነ እሁበክሙ አፈ ወጥበበ በዘኢይክሉ ተዋሥኦተ
ክሙ ወተዋቅሦተክሙ እለ ይትነሥኡ ላዕሌክሙ ።

፲፮ ወያገብኡክሙ አዝማዲክሙ ወአኃዊክሙ ወአዕርክ
ቲክሙ ወቢጽክሙ ።

፲፯ ወኵሉ ይጸልአክሙ በእንተ ስምየ ወይቀትሉክሙ ።

፲፰ ወኢትትኀጐል አሐቲ እምሥዕርተ ርእስክሙ ።

፲፱ ወበትዕግሥትክሙ ታጠርይዋ ለነፍስክሙ ።

## ክፍል ፻ወ፮ ፡ በእንተ ሙስናሃ ለኢየሩሳሌም ።

፳ ወአመ ርኢክሙ የዐግትዋ ሠራዊት ለኢየሩሳሌም
አእምሩ ከመ በጽሐ ሙስናሃ ።

፳፩ ወይእተ አሚረ እለ ውስተ ይሁዳ ይጕዩ ውስተ አድ
ባር ወእለሂ ማእከላ ይወጽኡ እምኔሃ ፡ ወእለሂ
ውስተ በሐውርቲሃ ኢይበውእዋ ።

፳፪ እስመ ዕድሜሃ ውእቱ በዘይትቤቀልዋ ከመ ይብጻሕ
ኵሉ ዘጽሑፍ ላዕሌሃ ።

፳፫ ወበሕቱ አሌ ሎን ለፅኑሳት ወለእለ የኀፅና በውእቱ
መዋዕል እስመ ይከውን ዐቢይ ምንዳቤ ዲበ ምድር
ወመቅሠፍት ዲበ ዝንቱ ሕዝብ ።

፳፬ ወይወድቁ በኵናት ወይፄወዉ ውስተ ኵሉ አሕዛብ
ወይከይድዋ አሕዛብ ለኢየሩሳሌም እስከ ይበጽሕ
ዕድሜሆሙ ለአሕዛብ ።



ነኝ ጊዜውም ደርሷል እያሉ በስሜ ይመጣሉና እን
ዳያስቷችሁ ተጠንቀቁ ተከትላችኋቸውም አትሂዱ ።
ማቴ ፳፬ ፡ ፬ ። ኤፌ ፫ ፡ ፮ ።
ጦርነቱን ፀብ ክርክሩን በሰማችሁ ጊዜ አትደንግጡ ፱
አስቀድሞ እንዲህ ይሆናልና ፤ ነገር ግን ያን ጊዜውኑ
የሚፈጸም አይደለም ።
ሕዝብ በሕዝብ ላይ ነገሥታትም በነገሥታት ላይ ፲
ይነሣሉ ። ማቴ ፳፬ ፡ ፯ ።
በየሀገሩ ረኃብ ታላቅ መነዋወጥ በሰውም ላይ ፍር ፲፩
ሃት ይመጣል በሰማይም ታላቅ ተአምር ይሆናል ።
ኢዮ ፫ ፡ ፫ ።
ከዚህም ሁሉ አስቀድሞ ይዘው ወደ አደባባይ ይወ ፲፪
ስዱ ችኋል አገር አስጥለው ያሳድዱ ችኋል ያስሯች
ኋል ፤ ስለ ስሜም ወደ ነገሥታትና ወደ መሳፍንት
ይወስዱ ችኋል ። ምዕ ፲፪ ፡ ፲፩ ። ማር ፲፫ ፡ ፱ ። ግብ
ሐዋ ፲፪ ፡ ፩ - ፱ ።
በእነሱ ምስክር ሊሆንባቸው ይህ መከራ ያገኛች ፲፫
ኋል ። ፊል ፩ ፡ ፲፱ ።
ዕወቁ የምትናገሩትን በልባችሁ አታስቡ ። ማቴ ፲ ፡ ፲፱ ። ፲፬
በእናንተ ላይ የተነሡት ጠላቶች ሊመልሱላችሁና ፲፭
ሊከራከሯችሁ እንዳይችሉ ዕውቀትንና አንደበትን
እሰጣችኋለሁ ። ግብ ሐዋ ፮ ፡ ፲ ።
ዘመዶቻችሁ ወንድሞቻችሁ ወዳጆቻችሁ ባልንጀሮ ፲፮
ቻችሁ አሳልፈው ይሰጧችኋል ። ሚክ ፯ ፡ ፮ ።
ሁሉም ስለ ስሜ ይጠሏችኋል ይገድሏችኋል ። ማቴ ፲፯
፲ ፡ ፳፩ - ፳፪ ።
ከራስ ጠጕራችሁ አንዲቱ አትጠፋም ። ምዕ ፲፪ ፡ ፯ ። ፲፰
በትዕግሥታችሁ ነፍሳችሁን ገንዘብ ታደርጓታላ ፲፱
ችሁ ። ፪ ዜና መዋ ፲፭ ፡ ፯ ። ዕብ ፲ ፡ ፴፮ ።

## ክፍል ፻፮ ፡ ስለ ኢየሩሳሌም ጥፋት ።

ኢየሩሳሌምን ወታደሮች ከበዋት ባያችሁ ጊዜ ፳
ጥፋቷ እንደ ደረሰ ዕወቁ ። ዳን ፱ ፡ ፳፮ ።
ያን ጊዜ በይሁዳ ያሉ ወደ ተራራ ይሸሹ ፤ በውስ ፳፩
ጧም ያሉ ከእሷ ይወጡ በአውራጃዎቿም ያሉ
ወደ ውስጧ አይገቡም ። ማቴ ፳፬ ፡ ፲፭ ።
በእሷ የተጻፈ ሁሉ ይፈጸም ዘንድ እሷን የሚበቀሉ ፳፪
በት ጊዜ ነውና ። ኤር ፭ ፡ ፳፱ ። ዳን ፱ ፡ ፳፮ - ፳፯
ነገር ግን በዚያ ወራት ለፀነሱ ወልደውም ለሚያሳ ፳፫
ድጉ ወዮላቸው ፤ በምድር ላይ ጽኑ መከራ ይሆና
ልና በዚህም ሕዝብ ላይ መቅሠፍት ይመጣልና ።
በጦር ይወድቃሉ በአሕዛብ ሁሉ ይማረካሉ ፤ አሕ ፳፬
ዛብ ጊዜያቸው እስኪፈጸም ድረስ ኢየሩሳሌምን
ይሠፍሩባታል ። ዘዳግ ፳፰ ፡ ፷፬ ። ሮሜ ፲፩ ፡ ፳፭ ።
ራዕ ፲፩ ፡ ፪ ።

## ክፍል ፻ወ፯ ፡ በእንተ እለ ይቀድሙ ትእምርታት ወበእንተ ምጽአቱ ለክርስቶስ ።

፳፭ ወይከውን ተእምር ውስተ ፀሐይ ወወርኅ ወከዋክብትኒ ይወድቁ እምሰማይ ዲበ ምድር ወይትመነደቡ አሕዛብ ወየኃሥሩ እምድምፀ ባሕር ፡ ወበሕርኒ ትደምፅ ወትትከወስ ።

፳፮ ወትወፅእ ነፍሰ እጓለ እመሕያው እምፍርሀት ወእምትሕዝብት ዘይመጽእ በዓለም እስመ ይትከወስ ኃይለ ሰማያት ይእተ አሚረ ።

፳፯ አሜሃ ይሬእይዎ ለወልደ እጓለ እመሕያው እንዘ ይመጽእ በደመና ሰማይ ምስለ ኃይል ብዙኅ ወስብሐት ።

፳፰ ወአመ ከነ ዝንቱ ኵሉ ስግዱ ወአንሥኡ ርእሰክሙ እስመ በጽሐ ዘያድኅንክሙ ።

፳፱ ወመሰለ ሎሙ ወይቤሎሙ እምከመ ርኢክምዋ ለበለስ ወለኵሉ ዕፀው ከመ ሠረፁ ተአምሩ ከመ አልጸቀ ማእረር ።

፴ ከማሁ አንትሙኒ እምከመ ርኢክሙ ከመ ከነ ዝንቱ አእምሩ ከመ በጽሐት መንግሥተ እግዚአብሔር ።

፴፩ አማን እብለክሙ ከመ ኢትኀልፍ ዛቲ ትውልድ እስከ አመ ይከውን ዝንቱ ኵሉ ።

፴፪ ሰማይ ወምድር የኃልፍ ወቃልየሰ ኢየኃልፍ ።

## ክፍል ፻ወ፰ ፡ ዘከመ ይደልዎሙ ለክርስቲያን ይንበሩ ድልዋኒሆሙ ።

፴፫ ዑቁ ርእሰክሙ ኢታክብዱ ልበክሙ በበሊዕ ወበስታይ ወበፈጊዕ ወበሐልዮ መንበርት ።

፴፬ ወትበጽሐክሙ ይእቲ ዕለት ግብተ ከመ መሥገርት እንተ ትወርድ ዲበ ኵሎሙ እለ ይነብሩ ዲበ ምድር ።

፴፭ ትጊሁ እንከ በኵሉ ጊዜ ከመ ትክሀሉ አምስጦ በጸሎትክሙ እምነ ዝንቱ ኵሉ ዘይመጽእ ወትቁሙ ቅድሜሁ ለወልደ እጓለ እመሕያው ።

፴፮ ወከነ መዓልተ ይሜህር በምኵራብ ወሌሊተ ይወፅእ ወይበይት ውስተ ደብረ ዘይት ዘስሙ ኤሌዎን ።

፴፯ ወኵሉ ሕዝብ ይገይሱ ኀቤሁ ውስተ ምኵራብ ያፅምዕዎ ቃሎ ።

## ክፍል ፻፯ ፡ ስለ ክርስቶስ መምጣትና ስለ መጀመሪያዎቹ ምልክቶች ።

በፀሐይና በጨረቃ ላይ ምልክት ይሆናል ከዋክብትም ከሰማይ ወደ ምድር ይወድቃሉ ከባሕር ድምፅ የተነሣ አሕዛብ ይጨነቃሉ ይጉሰቈላሉ ባሕርም ትበጠበጣለች ትናወጣለች ። ኢሳ ፲፫ ፡ ፲ ፡ መዝ ፵፯ ፡ ፬ ። ፳፭

በዓለም ላይ ከሚመጣው ከፍርሀትና ከሽብር የተነሣ የሰው ነፍስ ትለያለች ያን ጊዜ የሰማያት ኃይል ይናወጣልና ኢሳ ፳ ፡ ፯ ፤ ሕዝ ፳፬ ፡ ፳፫ ። ፳፮

ያን ጊዜም በሰማይ ደመና በፍጹም ኃይልና ጌትነት ሲመጣ የሰውን ልጅ ያዩታል ። ዳን ፯ ፡ ፲፫ ። ራእ ዮሐ ፩ ፡ ፯ ። ፳፯

ይህም ሁሉ በሆነ ጊዜ ስገዱና ራሳችሁን አንሡ የሚያድናችሁ መጥቷልና ። ሮሜ ፰ ፡ ፳፩-፳፫ ። ፊልጵ ፬ ፡ ፬-፭ ። ፳፰

ምሳሌም መስሎ እንዲህ አላቸው ፤ በለስን ዕንጨቶችን ሁሉ ለምልመው ባያችሁ ጊዜ መከር እንደ ደረሰ ዕወቁ ። ማቴ ፳፬ ፡ ፴፪ ። ፳፱

እንዲሁ እናንተም ይህ እንደሆነ ካያችሁ የእግዚአብሔር መንግሥት እንደ ደረሰች ዕወቁ ። ፴

ይህ ሁሉ እስኪደረግ ድረስ ይቺ ትውልድ እንደማታልፍ በእውነት እነግራችኋለሁ ። ፴፩

ሰማይና ምድር ያልፋል ፡ ቃሌ ግን አያልፍም ። ኢሳ ፶፩ ፡ ፯ ። ምዕ ፲፯ ፡ ፲፯ ። ፴፪

## ክፍል ፻፰ ፡ ለክርስቲያን ተዘጋጅተው መኖር እንደሚገባቸው ።

ራሳችሁን መርምሩ በመብል በመጠጥ በመቀማጠል ይህን ዓለም በማሰብ ልባችሁን አታደንድኑ ። ሮሜ ፲፫ ፡ ፲፫ ። ፩ ጴጥ ፬ ፡ ፯-፰ ። ገላ ፭ ፡ ፳፩ ። ፴፫

ያቺ ቀን በምድር በሚኖሩት ሁሉ ላይ እንደ ተዘረጋች ወጥመድ ሆና ድንገት ትደርስባችኋለች ። ፩ ተሰ ፭ ፡ ፳፩ ። ፴፬

ከዚህ ከሚመጣው ሁሉ በጸሎታችሁ ማምለጥ ትችሉ ዘንድ በሰው ልጅ ፊትም ትቆሙ ዘንድ ሁል ጊዜ ትጉ ። ኤር ፯ ፡ ፲፫ ። ፩ ተሰ ፭ ፡ ፯ ። ፪ ጴጥ ፫ ፡ ፲፩ ። ፩ ዮሐ ፪ ፡ ፳፰ ። ምዕ ፬ ፡ ፲፯ ። ፴፭

ቀን በምኵራብ ያስተምር ነበር ሌሊት ግን ወጥቶ ወይራማ በሚባል ተራራ ያድር ነበር ። ዮሐ ፰ ፡ ፩-፪ ። ፴፮

ሕዝቡም ሁሉ ቃሉን ሊሰሙ እሱ ወዳለበት ወደ ምኵራብ ማልደው ይሄዱ ነበር ። ሐጌ ፪ ፡ ፯ ። ሚል ፫ ፡ ፩ ። ፴፯

## ምዕራፍ ፳ወ፪ ።

### ክፍል ፪፻ወ፱ ፡ በእንተ ፋሲካ ።

፩ ወቀርበ በዓለ መጸለት ዘስሙ ፋሲካ ።

፪ ወየኀሥሡ ሊቃነ ካህናት ወጸሐፍት በዘይቀትልዎ
ወከኑ ይፈርህዎሙ ለሕዝብ ።

### ክፍል ፪፻ወ፲ ፡ በእንተ ይሁዳ ።

፫ ወቦአ ሰይጣን ውስተ ልበ ይሁዳ አስቆሮታዊ ዘእም
ዐሠርቱ ወክልኤቱ ኍልቁ ።

፬ ወሖረ ወተናገሮሙ ለሊቃነ ካህናት ወለጸሐፍት
ዘከመ ያገብኦ ሎሙ ።

፭ ወተፈሥሑ ወተሰነዐዉ ምስሌሁ ወተናገርዎ የሀብዎ
ሠላሳ ብሩረ ወእስተኀለቈ ነገረ ።

፮ ወየኀሥሥ ሳሕተ ያግብኦ ሎሙ እንዘ አልቦ ሰብእ ።

### ክፍል ፪፻፲ወ፩ ፡ በእንተ አስተዳልዎተ ፍሥሐ ።

፯ ወበጽሐት ዕለተ መጸለት አመ ይጠብሑ ፍሥሐ ።

፰ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ለጴጥሮስ ወለዮሐንስ
ሑሩ ወአስተዳልዉ ለነ ፍሥሐ ዘንበልዕ ።

፱ ወይቤልዎ በአይቴ ትፈቅድ ናስተዳሉ ለከ ፍሥሐ ።

፲ ወይቤሎሙ በዊአክሙ ሀገረ ትረክቡ ብእሴ ዘይፀ
ውር ጸሕበ ማይ ወትልውዎ ኪያሁ ኀበ ቦአ ቤተ ።

፲፩ ወበልዎ ለበዐለ ውእቱ ቤት ይቤለከ ሊቀ አይቴኑ
ቤት ኀበ እበልዕ ፍሥሐ ምስለ አርዳእየ ።

፲፪ ወውእቱ ያርእየክሙ ጽርሐ ዐቢየ ወንጹፈ ወሥር
ግወ ፡ ወበህየ አስተዳልዉ ለነ ።

፲፫ ወሖሩሮሙ ረከቡ በከመ ይቤሎሙ ወአስተዳለዉ
ፍሥሐ ።

### ክፍል ፪፻፲ወ፪ ፡ በእንተ ምሥጢረ ቍርባን ሐዲስ ።

፲፬ ወሶበ ኮነ ጊዜሁ ለድራር ረፈቀ እግዚእ ኢየሱስ
ወዐሠርቱ ወክልኤቱ ሐዋርያቲሁ ምስሌሁ ።

፲፭ ወይቤሎሙ ፈቲወ ፈተውክዎ ለዝንቱ ፋሲካ እብላዕ
ምስሌክሙ ዘእንበለ ይብጽሐኒ ሕማምየ ።

፲፮ እብለክሙ ባሕቱ ከመ ኢይበልዕ እንከ እምኔሁ
እስከ ይትፌጸም በመንግሥተ እግዚአብሔር ።

፲፯ ወተመጠወ ጽዋዐ ወአእኰተ ወይቤሎሙ ንሥኡ
ዘንተ ወተካፈልዎ ላዕሌክሙ ።



## ምዕራፍ ፳፪ ፡

### ክፍል ፪፻፱ ፡ ስለ ፋሲካ ።

ፋሲካ የሚባለው የቂጣ በዓል ቀርቦ ነበር ። ዘፀ ፩
፲፪ ፡ ፫ - ፳፰ ። ዘሌ ፳፫ ፡ ፭ - ፯ ። ማቴ ፳፮ ፡ ፩ - ፭ ።
የካህናት አለቆችና ጸፎችም ሊገድሉት ይሹ ነበር ፡ ፪
ግን ሕዝቡን ይፈሯቸው ነበር ። መዝ ፪ ፡ ፪ ። ዮሐ
፲፩ ፡ ፵፯ ። ግብ ሐዋ ፬ ፡ ፳፯ ።

### ክፍል ፪፻፲ ፡ ስለ ይሁዳ ።

ቍጥሩ ከዐሥራ ሁለት ወገን በነበረው በአስቆሮቱ ፫
ይሁዳ ልብ ሰይጣን ገባ ። ማቴ ፳፮ ፡ ፲፬ - ፲፭ ። ማር
፲፬ ፡ ፲ ።
ሄዶም እንዲያስይዛቸው የካህናት አለቆችንና ጸፎ ፬
ችን ተነጋገራቸው ።
ደስ ብሏቸው ከሱ ጋር ተስማምተው ሠላሳ ብር ሊሰ ፭
ጡት ተነጋገሩትና ነገር ቈረጡ ። ዘካ ፲፩ ፡ ፲፪ ።
፩ ጢሞ ፮ ፡ ፲ ። ፩ ዮሐ ፫ ፡ ፰ ።
ሰው ሳይኖር ለነሱ አሳልፎ ሊሰጠው ምቹ ጊዜ ይሻ ፮
ነበር ።

### ክፍል ፪፻፲፩ ፡ በጉን ስለ ማዘጋጀት ።

በጉን የሚያርዱበት የቂጣ በዓል ደረሰች ። ዘፀ ፲፪ ፡ ፯
፲፰ - ፳ ።
ጌታ ኢየሱስም ጴጥሮስንና ዮሐንስን ሂዱና የምን ፰
በላውን በጉን አዘጋጁልን አላቸው ።
በጉን ወዴት ልናዘጋጅልህ ትወዳለህ ? አሉት ። ፱
ወደ ሀገር በገባችሁ ጊዜ የውኃ ማድጋን የተሸከመ ፲
ሰው ታገኛላችሁና ወደሚገባበት ቤት ተከተሉት ።
የዚያን ቤት ጌታም መምህር ! ከደቀ መዛሙርቴ ጋር ፲፩
በጉን የምበላበት ቤት ወዴት ነው? ብሎሃል በሉት።
እሱም የተነጠፈ ያጌጠ ታላቅ ቤት ያሳያችኋል በዚያ ፲፪
አዘጋጁልን ። ማር ፲፬ ፡ ፲፭ ።
ሂደውም እንዳላቸው አገኙና በጉን አዘጋጁ ። ምዕ ፲፫
፲፱ ፡ ፴፪ ።

### ክፍል ፪፻፲፪ ፡ ስለ ሐዲስ የቍርባን ምሥጢር ።

የራት ሰዓት በሆነ ጊዜም ጌታ ኢየሱስ ለራት ተቀ ፲፬
መጠ ፡ ዐሥራ ሁለቱም ሐዋርያት ከርሱ ጋር ተቀ
መጡ ።
እንዲህም አላቸው ፡ መከራው ሳይደርስብኝ ይህን ፲፭
ፋሲካ ከናንተ ጋር ልበላ ወደድኩ ።
ነገር ግን በእግዚአብሔር መንግሥት እስኪፈጸም ፲፮
ድረስ እንግዲህ ከእሱ እንዳልበላ እነግራችኋለሁ ።
ምዕ ፲፫ ፡ ፳፱ ።
ጽዋውን ተቀብሎ አመስግኖ ይህን እንኩ ሁላች ፲፯
ሁም ተካፈሉት አላቸው ።

፩፻፲፬ ወንጌል ዘሉቃስ ፳፪ ።

፲፰ እብለክሙ ኢይሰቲ እንከ እምዝንቱ ፍሬ ወይን
እስከ አመ እሰትዮ ሐዲሰ በመንግሥተ እግዚአ
ብሔር ።
፲፱ ወነሥአ ኅብስተ ወአእኰቶ ፈተተ ወወሀቦሙ ወይቤ
ሎሙ ዝንቱ ውእቱ ሥጋየ ዘይትወሀብ በእንቲአ
ክሙ ለቤዛ ብዙኃን ወከመዝ ግበሩ ተዝካርየ በእን
ቲአየ ።
፳ ወከማሁ ጽዋዐኒ እምድኅረ ተደሩ ይቤሎሙ ዝንቱ
ጽዋዕ ዘሐዲስ ሥርዓት ደምየ ውእቱ ዘይትከዐው
በእንቲአክሙ ወበእንተ ብዙኃን ።

ክፍል ፻፲ወ፫ ፡ በእንተ ትእምርት ዘያገብኦ ።

፳፩ ወባሕቱ ናሁ እዴሁ ለዘያገብአኒ ምስሌየ ውስተ
ማእድ ።
፳፪ ወወልደ እጓለ እመሕያውሰ የሐውር በከመ ተሠርዐ
በእንቲአሁ ፡ ወባሕቱ አሌ ሎቱ ለውእቱ ብእሲ ዘበ
ውስተ እዴሁ ይትሜጠውዎ ለወልደ እጓለ እመ
ሕያው ።
፳፫ ወተባሀሉ አርዳኢሁ በበይናቲሆሙ መኑ እንጋ
ውእቱ እምኔሆሙ ዘዘንተ ይገብር ።

ክፍል ፻፲ወ፬ ፡ በእንተ ትሕትና ።

፳፬ ወእምዝ ተዋክሐ በበይናቲሆሙ እንዘ ይብሉ መኑ
እንጋ የዐቢ እምኔሆሙ ።
፳፭ ወይቤሎሙ ነገሥቶሙ ለአሕዛብ ይኴንንዎሙ ወይ
ቀንይዎሙ ወለመኳንንቲሆሙ ረዳእያነ ይብልዎሙ ።

፳፮ ወለክሙሰ አኮ ከመዝ አላ ዘየዓቢ እምኔክሙ ይኩ
ንክሙ ከመ ዘይንእስ ወሊቅኒ ይኩን ከመ ላእክ ።

፳፯ መኑ ውእቱ ዘየዐቢ ዘይረፍቅኑ ወሚመ ዘይትለ
አክ ፡ አኮኑ ዘይረፍቅ ፡ ወአንሰ ናሁ ከመ ላእክ በማእ
ከሌክሙ ።

፳፰ ወአንትሙሰ ባሕቱ እለ በእንቲአየ ተዓገሥክሙ
ምስሌየ በሕማምየ ።
፳፱ አነኒ አስተዳሉ ለክሙ መንግሥተ በከመ ሊተ ወሀ
በኒ አቡየ ።
፴ ከመ ትብልዑ ወትስተዩ በማእድየ በመንግሥትየ
ወትነብሩ ዲበ መናብርት ወትኴንኑ ዐሠርተ ወክል
ኤተ ሕዝበ እስራኤል ።

፴፩ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ለስምዖን ፡ ስምዖን ስምዖን
ናሁ ስኢለ ሰአለ ሰይጣን የሐንፅክሙ ወየኃንፍጽ
ክሙ ከመ ዐስስ ።

የሉቃስ ወንጌል ፳፪ ።

በእግዚአብሔር መንግሥት አዲሱን እስክጠጣው ፲፰
ድረስ እንግዲህ ከዚህ የወይን ፍሬ አልጠጣም እላ
ችኋለሁ ። ማቴ ፳፮ ፡ ፳፱ ።
ኅብስቱንም አንሥቶ አመስግኖ ቈርሶ ሰጣቸውና ፲፱
ስለ እናንተና ስለ ብዙዎች ቤዛ የሚሰጥ ሥጋዬ ይህ
ነው ፡ እኔ ስለ ሠራሁላችሁ መታሰቢያዬን እንዲህ
አድርጉ አላቸው ። ፩ ቆሮ ፲፩ ፡ ፳፫ ።
እንዲሁም ሥጋውን ከተቀበሉ በኋላ ፡ ሐዲስ ሥር ፳
ዓት የሚሆን ይህ ጽዋ ስለ እናንተ ነው አላቸው ። ዘፀ
፳፬ ፡ ፰ ። ዕብ ፲፪ ፡ ፳ - ፳፪ ።

ክፍል ፻፲፫ ፡ ስለሚያስይዘው የተሰጠ ምልክት ።

ነገር ግን የባላጋራዬ እጅ እነሆ በማእድ ላይ ነው ። ፳፩
መዝ ፵፩ ፡ ፲ ። ሚክ ፯ ፡ ፭ - ፯ ። ማር ፲፬ ፡ ፲፰ ።
የሰው ልጅስ ስለእርሱ እንደተጻፈ ይሞታል ፡ ነገር ፳፪
ግን የሰውን ልጅ በርሱ ለሚቀበሉበት ለዚያ ሰው
ወዮለት ! ። ኢሳ ፶፫ ፡ ፩ - ፲፪ ። ዳን ፱ ፡ ፳፬ ። ግብ
ሐዋ ፪ ፡ ፳፫ ።
ደቀ መዛሙርቱም ከመካከላቸው ይህንን የሚያደ ፳፫
ርግ ማን እንደሆነ እርስ በርሳቸው ተነጋገሩ ።
ማር፡ ፱ ፴፬ ። ሉቃ፡ ፱ ፵፮ ።

ክፍል ፻፲፬ ፡ ስለ ትሕትና ።

ከዚህ በኋላ ከነርሱ ማን ይበልጥ ማን ይበልጥ እያ ፳፬
ሉ እርስ በርሳቸው ተከራከሩ ። ምዕ፡ ፱ ፵፮ ።
እሱም እንዲህ አላቸው አሕዛብን ነገሥቶቻቸው ፳፭
ይገዟቸዋል እነሱም ገገርዎቻቸውን ረዳቶች ይሉአቸ
ዋል አላቸው ፡ ማቴ፡ ፳ ፳፭ - ፳፯ ። ማር፡ ፲ ፵፪ ።
ለእናንተ ግን እንዲህ አይደለም ፡ ከእናንተ ታላቁ ፳፮
እንደ ታናሽ አለቃውም እንደ አገልጋይ ይሁና
ችሁ እንጂ ። ፊል፡ ፪ ፫ ። ፩ ጴጥ፡ ፭ ፡ ፫ - ፯ ።
የሚበልጥ ማንኛው ነው? በማእድ ላይ የተቀመ ፳፯
ጠው ነው? ተቀምጦ የሚመገበው? ወይስ የሚላ
ከው? በማእድ የተቀመጠው አይደለምን? እነሆ
እኔም በመካከላችሁ እንደ አገልጋይ ነኝ ። ዮሐ፡
፲፫ ፬ - ፲፬ ።
እናንተስ መከራዬን ከእኔ ጋር ስለኔ የታገሣችሁ ፳፰
ናችሁ ። ምዕ፡ ፲፰ ፳፰ ። ዕብ፡ ፬ ፲፭ ።
እኔም አባቴ ለእኔ እንደሰጠኝ መንግሥትን አዘጋ ፳፱
ጅቼላችኋለሁ ። ያዕ፡ ፪ ፭ ። ራእ፡ ዮሐ፡ ፫ ፳፩ ።
በመንግሥቴ በማእዴ ትበሉ ትጠጡ ዘንድ በወን ፴
በር ተቀምጣችሁ በሀሥራ ሁለቱ ነገደ እስራኤል
ትፈርዳላችሁ ። ፪ ሳሙ፡ ፱ ፱ ። ፪ ሳሙ፡ ፲፱ ፳፰ ።
ማቴ፡ ፲፱ ፳፰ ።
ጌታ ኢየሱስም ስምዖንን እንዲህ አለው ፤ ስምዖን ! ፴፩
ስምዖን ! ሰይጣን እንደ አጃ ሊጠረጥራችሁ ሊያጓል
ብችሁ አሁን ለመናን ለመነ አለው ። ማቴ፡ ፳፮
፴፩ - ፴፭ ። አሞ፡ ፱ ፱ ። ፩ ጴጥ፡ ፭ ፰ ።

ፍርሃቶሙ ለአይሁድ ከመ ይትነሣእ ሥጋሁ ለእግ
ዚእ ኢየሱስ፡ ወአብሖ ጲላጦስ ወሖረ ውእቱኒ ወነ
ሥአ ሥጋሁ ለእግዚእ ኢየሱስ ።

፴፱ ወመጽአ ኒቆዲሞስኒ ዘሖረ ኀቤሁ ለእግዚእ ኢየሱስ
ቀዲሙ ሌሊተ ወአምጽአ ምእተ ልጥረ ከርቤ ወዓ
ልወ ሕዉሰ በዘበቱ ይቀብርዎ ።

፵ ወነሥኡ ሥጋሁ ለእግዚእ ኢየሱስ ወገነዝዎ በመዋ
ጥሐ ክታን ዘሰንዱናት ምስለ አፈው በከመ ሕገ
አይሁድ ሰበ ይገንዙ ወይቀብሩ ።
፵፩ ወቦ ህየ ገነት ውስተ ውእቱ መካን ኀበ ሰቀልዎ
ወውስተ ውእቱ ገነት ዝኅር ሐዲስ ዘአልቦ ዘተቀ
ብረ ውስቴቱ ።

፵፪ ወህየ ቀበርዎ ለእግዚእ ኢየሱስ እስመ ተፍጻሜተ
ዐርበሙ ውእቱ ለአይሁድ፡ ወቅሩብ ውእቱ መቃ
ብር ኀበ ሰቀልዎ ።

ምዕራፍ ፳ ።

<u>ክፍል ፵ በእንተ እለ ሖሩ ኀበ መቃብር ።</u>

፩ ወበእሑድ ሰንበት መጽአት ማርያም መግደላዊት
በጽባሕ ኀበ መቃብር እንዘ ዓዲሁ ጽልመት ወረከ
በት እብነ እቱተ እምአፈ መቃብር ።

፪ ወሮፀት ወበጽሐት ኀበ ስምዖን ጴጥሮስ ወኀበ ዝኩ
ካልእ ረድእ ዘያፈቅሮ እግዚእ ኢየሱስ፡ ወትቤሎሙ
ነሥእዎ ለእግዚእየ እምውስተ መቃብር ወኢየአ
ምር ኀበ ወሰድዎ ።
፫ ወወፅኡ ጴጥሮስ ወዝኩኒ ካልእ ረድእ ወሖሩ ኀበ
መቃብር ።
፬ ወእንዘ ይረውፁ ክልኤሆሙ ኅቡረ በደሮ ለጴጥሮስ
ዝኩ ካልእ ረድእ በጺሐ ኀበ መቃብር ።
፭ ወሶበ ሐወጸ ርእየ መዋጥሐ ንቡረ ወኢቦአ ባሕቱ ።

፮ ወተለዎ ስምዖን ጴጥሮስ ወበጽሐ ወቦአ ውስተ
መቃብር ወረከበ መዋጥሐ ንቡረ ውስተ አሐዱ ገጽ ።
፯ ወሰበንኒ ዘዲበ ርእሱ እንተ ባሕቲቱ ጥብሉለ ወአኮ
ምስለ መዋጥሕ ።
፰ ወእምዝ ቦአ ዝኩኒ ካልእ ረድእ ዘበደሮ በጺሐ ኀበ
መቃብር ወርእዩ ወአምኑ ።

፱ እስመ ዓዲሁ ኢያእመሩ ዘውስተ መጻሕፍት ከመ
ሀለዎ ይትነሣእ እምነ ምውታን ።

፲ ወእምዝ ሖሩ ክልኤሆሙ አርዳኢሁ ወአተዉ
ቤቶሙ ።



ዮሴፍ የጌታ ኢየሱስን ሥጋ ይወስድ ዘንድ ጲላጦ
ስም ለመነና ፈቀደለት፡ እሱም ሄዶ የጌታ ኢየሱስን
ሥጋ ወሰደ ። ማቴ ፳፯ ፡ ፶፯ - ፷፩ ። ማር ፲፭ ፡
፵፪ - ፵፯ ። ሉቃ ፳፫ ፡ ፶ - ፶፭ ።
ቀድሞ በሌሊት ወደ ጌታ ኢየሱስ ሄዶ የነበረው ፴፱
ኒቆዲሞስም መጥቶ ገንዘው የሚቀብሩበትን መቶ
ንጥር ከርቤ ቅልቅል ሽቱ አመጣ። ፪ ዜና መዋ ፲፮ ፡
፲፬ ። ምዕ ፫ ፡ ፩ - ፪ ። ሉቃ ፳፫ ፡ ፶፮ ።
የጌታ ኢየሱስንም ሥጋ ወስደው በሚገንዙበትና በሚ ፵
ቀብሩት ጊዜ አይሁድ እንደሚያደርጉት ሕግ ከሽቱ
ጋር በድርብ በፍታ ገነዙት ። ግብ ሐዋ ፭ ፡ ፮ ።
በሰቀሉበት በዚያም ቦታ የአትክልት ሥፍራ ነበር ፵፩
በዚያ በአታክልቱም ቦታ በውስጡ የተቀበረ ሰው
የሌለበት አዲስ መቃብር ነበር ። ፪ ነገ ፳፫ ፡ ፲፮ ።
ኢሳ ፳፪ ፡ ፲፮ ።
ጌታ ኢየሱስን ከዚያ ቀበሩት፡ ለአይሁድ የመሰናዶ ፵፪
አቸው ፍጻሜ ነበርና መቃብሩ ለሰቀሉበት ቅርብ
ነበር ።

ምዕራፍ ፳ ፤

<u>ክፍል ፵ ፡ ወደ መቃብር ስለ ሄዱ ሰዎች ።</u>

በእሑድ ሰንበት ማርያም መግደላዊት ገና ጨለማ ፩
ሳለ ገሥግሣ ወደ መቃብር መጣችና ደንጊያውንም
ከመቃብሩ አፍ ተነሥቶ አገኘች። ማቴ ፳፰ ፡ ፩ ።
ማር ፲፮ ፡ ፩ ። ሉቃ ፳፬ ፡ ፩ ።
ሮጣም ወደ ስምዖን ጴጥሮስና ጌታ ኢየሱስ ይወ ፪
ደው ወደ ነበረው ወደዚያ ወደ ሁለተኛው ደቀ መዝ
ሙር ደርሳ ጌታዬን ከመቃብር ወስደዉታል፡ የወሰ
ዱበትንም አላውቅም አለቻቸው ። ምዕ ፲፫ ፡ ፳፫ ።
ጴጥሮስና ያ ደቀ መዝሙርም ወጡና ወደ መቃብር ፫
ሄዱ ። ሉቃ ፳፬ ፡ ፲፪ ።
ሁለቱም በአንድነት ሲሮጡ ያ ሌላው ደቀ መዝሙር ፬
ጴጥሮስን ቀድሞት ወደ መቃብር ደረሰ ።
በተመለከተም ጊዜ መግነዙን ተቀምጦ አየ፡ ነገር ፭
ግን አልገባም ። ምዕ ፲፱ ፡ ፵ ።
ስምዖን ጴጥሮስም ተከትሎት ደረሰና ወደ መቃብር ፮
ገባ፡ ከፈኑንም ባንድ ወገን ተጠቅልሎ አገኘ ።
በራሱ ላይ የነበረው መጠምጠሚያም ለብቻው ተጠ ፯
ቅልሎ ነበር እንጂ ከከፈኑ ጋር አልነበረም ።
ከዚህም በኋላ ያ ጴጥሮስን ቀድሞት ወደ መቃብር ፰
የደረሰው ሌላው ደቀ መዝሙር ገባ፡ አይተውም
አመኑ ።
ከሙታን ተለይቶ ይነሣ ዘንድ እንደ ነበረው ገና ፱
አላወቁም ነበርና ። መዝ ፲፮ ፡ ፲ ። ኢሳ ፳፮ ፡ ፲፱ ።
ቆሮ ፲፭ ፡ ፬ ።
ከዚህ በኋላ ሁለቱ ደቀ መዝሙርቱ ተመልሰው ወደ ፲
ቤታቸው ገቡ ።

ክፍል ፵ወ፩ ፡ በእንተ ዘከመ አስተርአየ ለማርያም መግደላዊት ።

፲፩ ወማርያምሰ ቆመት ኀበ መቃብር አፍአ ወትበኪ ፡ ወእንዘ ትበኪ ሐወጸት ውስተ መቃብር ።

፲፪ ወርእየት ክልኤተ መላእክተ በፀዐድው አልባስ ወይነብሩ አሐዱ ትርአሰ ወአሐዱ ትርጋፀ ኀበ ነበረ ሥጋሁ ለእግዚእ ኢየሱስ ።

፲፫ ወይቤልዋ እሙንቱ መላእክት ምንት ያበክየኪ አብእሲቶ ወመነ ተኃሥሢ ወትቤሎሙ ነሥእዎ ለእግዚእየ እምውስተ መቃብር ወኢየአምር ኀበ ወሰድዎ ።

፲፬ ወዘንተ ብሂላ ተመይጠት ድኅሬሃ ወርእየቶ ለእግዚእ ኢየሱስ እንዘ ይቀውም ፡ ወኢያእመረት ከመ እግዚእ ኢየሱስ ውእቱ ።

፲፭ ወይቤላ እግዚእ ኢየሱስ ብእሲቶ ምንት ያበክየኪ ወመነ ተኃሥሢ ፡ ወመሰላ ላቲሰ ዐቃቤ ገነት ውእቱ፡ ወትቤሎ እግዚእየ እመኒ አንተ ነሣእኮ ንግረኒ ኀበ ወሰድኮ ከመ እሑር እነ ወእንሥኦ ኀቤየ ወእቅብኦ ዕፍረተ ።

፲፮ ወይቤላ እግዚእ ኢየሱስ "ማርያም" ፡ ወተመይጠት ወትቤሎ በነገረ ዕብራይስጥ ረቡኒ ዘበትርጓሜሁ ሊቅ ብሂል ።

፲፯ ወይቤላ እግዚእ ኢየሱስ ኢትልክፍኒ እስመ ዓዲ ኢዓረጉ ኀበ አቡየ ወሑሪ ባሕቱ ኀበ አኅውየ ወበሊዮሙ አዐርግ ኀበ አቡየ ወአቡክሙ ኀበ አምላኪየ ወአምላክክሙ ።

፲፰ ወሖረት ማርያም መግደላዊት ወአብሠረቶሙ ለአርዳኢሁ ወትቤሎሙ ርኢክዎ ለእግዚእነ ወነገረቶሙ ዘከመ ይቤላ ።

ክፍል ፵ወ፪ ፡ ዘከመ አስተርአዮሙ ለሐዋርያት ።

፲፱ ወመስዮ ውእቱ ዕለት ዘውእቱ እሑድ ሰንበት እንዘ ዕፁው ኆኅት ኀበ ሀለዉ አርዳኢሁ ጉቡአን በእንተ ፍርሃቶሙ ለአይሁድ መጽአ እግዚእ ኢየሱስ ወቆመ ማእከሎሙ ወይቤሎሙ ሰላም ለክሙ ።

፳ ወዘንተ ብሂሎ አርአዮሙ እደዊሁ ወእገሪሁ ወገቦሁ ወተፈሥሑ አርዳኢሁ ሶበ ርእይዎ ለእግዚእነ ።

፳፩ ወካዕበ ይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ሰላም ለክሙ ወበከመ ፈነወኒ አብ ከማሁ አነኒ እፌኑወክሙ ።

፳፪ ወዘንተ ብሂሎ ነፍሐ ላዕሌሆሙ ወይቤሎሙ ንሥኡ መንፈሰ ቅዱሰ ።

፳፫ ለእለ ኃደግሙ ኃጢአተ ይትኃደግ ሎሙ ፡ ወለእለሰ ኢኃደግሙ ኢይትኃደግ ሎሙ ።



ክፍል ፵፩ ፡ ለማርያም መግደላዊት ስለ መገለጡ ።

፲፩ ማርያም ግን ከመቃብሩ በስተውጭ እያለቀሰች ቆማ ነበረ ፡ እያለቀሰችም ወደ መቃብር ተመለከተች ።

፲፪ ሁለቱ መላእክትንም ነጭ ልብስ ለብሰው የጌታ ኢየሱስ ሥጋ በነበረበት በታ አንዱ በራስጌ አንዱ በግርጌ ተቀምጠው አየች ።

፲፫ እነዚያ መላእክትም አንቺ ሴት ምን ያስለቅስሻል ? ማንንስ ትሺ አለሽ? አሏት ፡ ጌታዬን ከመቃብር ውስጥ ወስደዉታል የወሰዱበትንም አላውቅም አለቻቸው ።

፲፬ ይህንንም ተናግራ ወደ ኋላዋ መለስ ብላ ጌታ ኢየሱስን ቆሞ አየችው ፡ ግን ጌታ ኢየሱስ እንደሆነ አላወቀችም ። ማቴ ፳፰ ፡ ፱ ።

፲፭ ጌታ ኢየሱስም አንቺ ሴት ! ምን ያስለቅስሻል ? ማንንስ ትሺ አለሽ ? አላት ፡ እርሷ ግን ያትክልቱ በታ ጠባቂ መስሏት ነበር ፡ ጌታዬ ! አንተ ወስደኸው እንደሆነ ሂጄ ወደኔ አምጥቼ ሽቱ እንድቀባው የወሰድክበትን ንገረኝ አለቺው ።

፲፮ ጌታ ኢየሱስም "ማርያም" ! አላት ፡ እርሷ መለስ ብላ በዕብራይስጥ ቋንቋ ረቡኒ አለቺው ፡ ትርጓሜውም መምህር ማለት ነው ። ማር ፲ ፡ ፶፩ ። ምዕ ፩ ፡ ፴፰-፴፱ ።

፲፯ ጌታ ኢየሱስም አትንኪኝ ፡ ገና ወደ አባቴ አላረግሁምና ፡ ነገር ግን ወደ ወንድሞቼ ሂደሽ ወደ አባቴ ወደ አባታችሁ ፡ ወደ አምላኪዬ ወደ አምላካችሁ ዐርጋለሁ አለ ብለሽ ንገሪአቸው ። መዝ ፳፪ ፡ ፳፪ ። ዕብ ፪ ፡ ፲፩ ። ምዕ ፲፮ ፡ ፳፰ ።

፲፰ ማርያም መግደላዊትም ሂዳ የምሥራች አለቻቸው ጌታችንን አየሁት ብላም እንዳላት ነገረቻቸው ።

ክፍል ፵፪ ፡ ለሐዋርያት ስለ መገለጡ ።

፲፱ ያም ቀን ማለት እሑድ የተባለው ሰንበት በመሸ ጊዜ ደጁ ተዘግቶ ሳለ ደቀ መዛሙርቱ አይሁድን ስለ ፈሩ ተሰብስበው ወደ ነበሩበት በታ ጌታ ኢየሱስ መጥቶ በመካከላቸው ቆመና ሰላም ለእናንተ ይሁን አላቸው ። ማር ፲፮ ፡ ፲፬ - ፲፰ ።

፳ ይህንንም ብሎ እጁን እግሩንና ጐኑን አሳያቸው ደቀ መዛሙርቱም ጌታችንን ባዩት ጊዜ ደስ አላቸው ። ምዕ ፲፱ ፡ ፴፬ ። ፩ ዮሐ ፩ ፡ ፩ ።

፳፩ ጌታ ኢየሱስም ዳግመኛ ሰላም ለእናንተ ይሁን ፡ አብ እኔን እንደላከኝ እንዲሁ እኔም እናንተን እልካችኋለሁ አላቸው ። ኢሳ ፷፩ ፡ ፩ ። ፲፯ ፡ ፲፰ ።

፳፪ ይህንንም ብሎ እፍ አለባቸውና ፡ መንፈስ ቅዱስን ተቀበሉ አላቸው ።

፳፫ ይቅር ላላችሁላቸው ኃጢአታቸው ይሠረይላቸዋል ፡ ይቅር ላላላችሁላቸውም አይሠረይላቸውም ።

## ክፍል ፺ወ፫ ፥ በእንተ ቶማስ ።

፳፬ ወቶማስ አሐዱ እምዐሠርቱ ወአሐዱ አርዳኢሁ ዘይብልዎ ዲዲሞስ ኢሀሎ ምስሌሆሙ ሶበ መጽአ እግዚእ ኢየሱስ ።

፳፭ ወይቤልዎ ካልኣኒሁ አርዳእ ርኢናሁ ለእግዚእነ ፥ ወይቤሎሙ እመ ኢርኢኩ አደዊሁ ወእገሪሁ ኀበ ቀነውዎ ወእመ ኢወደይኩ አጽባዕትየ ውስተ ቅንዋቲሁ ወእመ ኢያበእኩ እዴየ ውስተ ገቦሁ ኢየአምን ።

፳፮ ወእምድኅረ ሰሙን መዋዕል እንዘ ሀለዉ ካዕበ አርዳኢሁ ውስጠ ወቶማስኒ ሀሎ ምስሌሆሙ እንዘ ዕፁዋኖት መጽአ እግዚእ ኢየሱስ ወቆመ ማእከሎሙ ፡ ወይቤሎሙ ሰላም ለክሙ ።

፳፯ ወእምዝ ይቤሎ ለቶማስ አምጽእ አጽባዕተከ ዝየ ወርኢ እደውየ ወእገርየ ወሀብ እዴከ ወአብእ ውስተ ገቦየ ወግሥሥኒ ወኢትኩን ናፋቄ አላ እመን ።

፳፰ ወአውሥአ ቶማስ ወይቤሎ እግዚእየ ወአምላኪየ ።

፳፱ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ እስመ ርኢከኒ አመንከኒ ፡ ብፁዓንሰ እንዘ ኢይሬእዩኒ የአምኑኒ ።

፴ ወብዙኃተ ካልአተ ተአምራተ ገብረ እግዚእ ኢየሱስ በቅድመ አርዳኢሁ ዘኢተጽሕፈ ውስተ ዝንቱ መጽሐፍ ።

፴፩ ወዝንቱሰ ተጽሕፈ እምኔሆን ከመ ትእመኑ አንትሙ ከመ ኢየሱስ ክርስቶስ ውእቱ ወልደ እግዚአብሔር ፥ ወእሚነክሙ ሕይወተ ዘለዓለም ትርከቡ በስመ ዚአሁ ።

### ምዕራፍ ፳ወ፩ ።

## ክፍል ፺ወ፬ ፡ ዘከመ አስተርአዮሙ ለሐዋርያት በባሕረ ጥብርያዶስ ።

፩ ወእምዝ ካዕበ አስተርአዮሙ እግዚእ ኢየሱስ ለአርዳኢሁ በብሔረ ጥብርያዶስ ወከመዝ አስተርአዮሙ ።

፪ እንዘ ሀለዉ ኅቡረ ስምዖን ጴጥሮስ ወቶማስ ዘይብልዎ ዲዲሞስ ወናትናኤል ዘቃና ዘገሊላ ወደቂቀ ዘብዴዎስ ወዓዲ ካልኣን ክልኤቱ እምውእቶ አርዳኢሁ ።

፫ ወይቤሎሙ ስምዖን ጴጥሮስ አንሰ አሐውር ከመ አሥግር ዓሣ ፡ ወይቤልዎ ካልኣኒሁ አርዳእ ንሕነኒ ንመጽእ ምስሌከ ወሖሩ ወዐርጉ ሐመረ ወአልበ ዘአሥገሩ በይእቲ ሌሊት ወኢምንተኒ ።



## ክፍል ፺፫ ፥ ስለ ቶማስ ።

ከዐሥራ አንዱ ደቀ መዛሙርቱ አንዱ ዲዲሞስ የሚሉት ቶማስ ጌታ ኢየሱስ በመጣ ጊዜ ከደቀ መዛሙርቱ ጋር አልነበረም ። ፳፬
ጓደኞቹ ደቀ መዛሙርትም ጌታችንን አየነው አሉት ፳፭
የቸነከሩትን እጆቹን እግሮቹን ካላየሁ ጣቴንም ወደ ችንካሮቹ ካልጨመርኩ እጄንም ወደ ጐኑ ካላገባሁ አላምንም አላቸው ።

ከስምንት ቀን በኋላም ደቀ መዛሙርቱ በውስጥ ፳፮
ሳሉ ፥ ቶማስም አብሯቸው ሳለ በሩ ተዘግቶ ሳለ ዳግመኛ ጌታ ኢየሱስ በመካከላቸው ቁሞ ሰላም ለእናንተ ይሁን አላቸው ። ቍ ፲፱ ።
ከዚህም በኋላ ፡ ቶማስን ጣትህን ወዲህ አምጣና ፳፯
እጆቼንና እግሮቼን እይ ፥ እጅህንም አምጣና ወደ ጐኔ አግብተህ ዳስሰኝ ፡ እመን እንጂ ተጠራጣሪ አትሁን አለው ። ፩ ዮሐ ፩ ፡ ፩ ።
ቶማስም መልሶ ጌታዬ አምላኬ ! አለው ። ፳፰
ጌታ ኢየሱስም ቶማስ ! ስላየኸኝ አመንክብኝን ? ፳፱
ብፁዓንስ ሳያዩኝ የሚያምኑብኝ ናቸው አለው ።
፪ ቆሮ ፭ ፡ ፯ ። ፩ ጴጥ ፩ ፡ ፰ ።
ጌታ ኢየሱስም በዚህ መጽሐፍ ያልተጻፈ በደቀ ፴
መዛሙርቱ ፊት ሌላ ብዙ ተአምራት አደረገ ፡ ምዕ ፳፩ ፡ ፳፭ ።
ነገር ግን ይህ ኢየሱስ ክርስቶስ የእግዚአብሔር ፴፩
ልጅ እንደ ኾነ እናንተ ታምኑ ዘንድ አምናችሁም በርሱ ስም የዘላለም ሕይወትን ታገኙ ዘንድ ተጻፈ ። ፩ ዮሐ ፭ ፡ ፲፫ ።

### ምዕራፍ ፳፩ ፡

## ክፍል ፺፬ ፡ ለሐዋርያት በጥብርያዶስ ባሕር ስለ መገለጡ ።

ከዚህም በኋላ ጌታ ኢየሱስ ጥብርያዶስ አገር ለደቀ ፩
መዛሙርቱ እንደገና ታያቸው ፥ እንዲህም ተገለጸላቸው ።
ስምዖን ጴጥሮስ ፥ ዲዲሞስ የሚሉት ቶማስ ፥ የቃና ፪
ዘገሊላ ናትናኤል የዘብዴዎስ ልጆች ሌሎችም ከደቀ መዛሙርቱ ሁለት አብረው ሳሉ ። ምዕ ፭ ፡ ፺፮ ።
ማቴ ፬ ፡ ፳፩ ።
ስምዖን ጴጥሮስም እኔ ዓሣ ላጠምድ እሄዳለሁ አላቸው ፫
ሌሎች ደቀ መዛሙርትም እኛም ከንተ ጋር እንመጣለን ብለው በመርከብ ተሳፍረው ሄዱ ፡ ግን በዚያች ሌሊት ምንም የያዙት የለም ።

ወንጌል ዘዮሐንስ ፳፩ ።

፬ ወጸቢሖ ይቀውም እግዚእ ኢየሱስ ውስተ ሐይቅ
ወርእይዎ አርዳኢሁ ወኢያእመሩ ከመ እግዚእ ኢየ
ሱስ ውእቱ ።
፭ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ደቂቅየ ቦኑ ብከሙ
ዘንበልዕ ፡ ወይቤልዎ አልቦ ።
፮ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አውርዱ መሣግሪክሙ
ኀበ ይምነ ሐመር ወትረክቡ ብዙኃ ፡ ወይቤልዎ
ሠራሕነ ኵላ ሌሊተ ወአልቦ ዘረከብነ ወኢምንተኒ
ወበቃልከሰ ናወርድ ፡ ወአውረዱሙ መሣግሪሆሙ
ስእኑ እንከ ስሒበ እምብዝኃ ዓሣት ዘተሠግረ ።
፯ ወይቤሎ ለጴጥሮስ ዝኩ ካልእ ረድእ ዘያፈቅሮ እግ
ዚእ ኢየሱስ እግዚእነ ውእቱ ፡ ወሰሚዖ ስምዖን ጴጥ
ሮስ ከመ እግዚእነ ውእቱ ነሥአ ሰንዱነ ዘይትዓፀፍ
ወቀነተ ውስተ ሐቌሁ እስመ ዕራቁ ውእቱ ወተወ
ርወ ውእቱ ውስተ ባሕር ።
፰ ወካልአንሰ አርዳእ በሐመር በጽሑ እስመ ኢኮኑ
ርኁቃነ እምድር ዘእንበለ መጠነ ክልኤ ምእት በእ
መት ወሐሩ እንዘ ይስሕቡ መሣግሪሆሙ ዘውስቴ
ቶን ዓሣት ።
፱ ወወሪዶሙ ምድረ ረከቡ ፍሕመ ብቊጸ ወዓሣ ጥቡሰ
ወኅብስተ ሥሩዓ ።
፲ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አምጽኡ እምዓሣት
ዘአኀዝክሙ ይእዜ ።
፲፩ ወዐርገ ስምዖን ጴጥሮስ ውስተ ሐመር ወሰሐበ መሥ
ገርተ ውስተ ምድር ወምሉእ ውስቴቱ ዓሣተ ዐበ
ይተ ምእተ ወኃምሳ ወሠለስተ ፡ ወእንዘ መጠነዝ
ብዝኁ ኢተሰጠ መሥገርቱ ።
፲፪ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ንዑ ንምሳሕ ፡ ወአልቦ
ዘተኀበለ እምአርዳኢሁ ይሰአሎ ወይበሎ መኑ አንተ
እስመ አእመሩ ከመ እግዚእነ ውእቱ ።
፲፫ ወመጽአ እግዚእ ኢየሱስ ወነሥአ ኅብስተ ወወሀ
በሙ ፡ ወእምዓሣሁኒ ከማሁ ።
፲፬ ወዝንቱ ሣልሱ እንዘ ያስተርእዮሙ እግዚእ ኢየሱስ
ለአርዳኢሁ እምድኅረ ተንሥአ እምነ ምዉታን ።

ክፍል ፺ወ፭ ፡ በእንተ ሢመቱ ለጴጥሮስ ።

፲፭ ወእምድኅረ መስሐ ይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ለስም
ዖን ጴጥሮስ ፡ ስምዖን ወልደ ዮና ታፈቅረኒኑ ፈድፋደ
እምእሉ ፡ ወይቤሎ እወ እግዚኦ ለሊከ ተአምር ከመ
አነ አፈቅረከ ፡ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ረዐይኬ
አባግዕየ ።
፲፮ ወካዕበ ይቤሎ ዳግመ ስምዖን ወልደ ዮና ታፈቅረ

የዮሐንስ ወንጌል ፳፩ ።

በነጋ ጊዜም ጌታ ኢየሱስ ከወደቡ ቁሞ ነበር ፡ ደቀ ፬
መዛሙርቱ አዩት ፡ ግን ጌታ ኢየሱስ እንደሆነ አላ
ወቁም ። ምዕ ፳ ፡ ፲፱ ። ሉቃ ፳፬ ፡ ፲፮ ።
ጌታ ኢየሱስም ልጆቼ! የምንበላው አላችሁን ? ፭
አላቸው ፤ የለም አሉት ። ሉቃ ፳፬ ፡ ፵፩ ።
ጌታ ኢየሱስ መረባችሁን ከመርከቡ በስተቀኝ በኩል ፮
ጣሉ ብዙ ታገኛላችሁ አላቸው ፡ መላ ሌሊቱን ደከ
ምን ምንም ያገኘነው የለም ፡ ግን ባንተ ቃል መረ
ቡን እንጥላለን አሉት ፡ መረባቸውን በጣሉ ጊዜ ከተ
ያዘው ዓሣ ብዛት የተነሣ ስቦ ማውጣት ተሳናቸው ።
ጌታ ኢየሱስ ይወደው የነበረ ያ ሌላው ደቀ መዝ ፯
ሙርም ለጴጥሮስ ጌታችን ነው አለው ፤ ስምዖን ጴጥ
ሮስም ጌታችን እንደሆነ ባወቀ ጊዜ የሚለብሰውን
ልብስ አንሥቶ ወገቡን ታጠቀ ፡ ራቁቱን ነበርና ወደ
ባሕርም ተወረወረ ። ምዕ ፲፫ ፡ ፳፫ ።
ሌሎች ደቀ መዛሙርት ግን በታንኳ መጡ ፡ ከሁለት ፰
መቶ ክንድ ያህል በቀር ከምድር አልራቁም ነበርና
ዓሣ የተመሉ መረቦቻቸውን እየሳቡ ሄዱ ።

ወደ ምድርም በወረዱ ጊዜ ፍሙ መርቶ ዓሣው ፱
ተጠብሶ ማእዱ ተሠርቶ አገኙት ።
ጌታ ኢየሱስም አሁን ከያዛችሁት ዓሣ አምጡ ፲
አላቸው ።
ስምዖን ጴጥሮስም ወደ ታንኳው ወጥቶ መረብን ፲፩
ስቦ ወደ ምድር አወጣ ፡ በውስጡም ዓሣ መልቶበት
ነበር ፤ መቶ ኃምሳ ሦስት ታላላቅ ዓሣ ይዞ ነበር ፤
ብዛቱ ይህን ያህል ሲሆንም መረቡ አልተቀደደም ።
ጌታ ኢየሱስም ኑ ምሳ እንብላ አላቸው ፡ ከደቀ ፲፪
መዛሙርቱም አንተ ማነህ? ብሎ ሊጠይቀው የደፈረ
የለም ጌታችን እንደ ኾነ አውቀዋልና ። ግ ሐ ፲ ፡ ፵ ።
ጌታ ኢየሱስም ቀረብ ብሎ ኅብስቱን አንሥቶ ሰጣ ፲፫
ቸው ፡ ከዓሣውም እንዲሁ ። ምዕ ፮ ፡ ፲ ።
ጌታ ኢየሱስ ከሙታን ተለይቶ ከተነሣ በኋላ ለደቀ ፲፬
መዛሙርቱ ሲታያቸው ይህ ሦስተኛው ነው ። ምዕ
፳ ፡ ፲፱ - ፳፮ ።

ክፍል ፺፭፡ ስለ ጴጥሮስ ሹመት ።

ምሳም ከበሉ በኋላ ጌታ ኢየሱስ ስምዖን ጴጥሮስን ፲፭
የዮና ልጅ ስምዖን ! ከእነዚህ ይበልጥ ትወደኛለህን?
አለው ፡ እሱም አዎን አቤቱ! እኔ እንደምወድህ አንተ
ታውቃለህ አለው ፡ ጌታ ኢየሱስም በጎቼን ጠብቅ
አለው ። ፪ ነገ ፳፫ ። ምዕ ፩ ፡ ፵፪ ።
ዳግመኛም የዮና ልጅ ስምዖን ! ትወደኛለህን ? አለው ፲፮

ኒኑ ፡ ወይቤሎ እወ እግዚኦ አንተ ተአምር ከመ አነ አፈቅረከ ፡ ወይቤሎ ረዐይኬ መሐስእየ ።

፲፯ ወይቤሎ ሣልሰ ስምዖን ወልደ ዮና ታፈቅረኒኑ ወተከዘ ጴጥሮስ እስመ ይቤሎ ሣልሰ ታፈቅረኒኑ ፡ ወይቤሎ እግዚኦ ለሊከ ተአምር ኵሎ ወለሊከ ትጤይቅ ከመ አነ አፈቅረከ ፡ ወይቤሎ ረዐይኬ አባግዕየ ።

፲፰ አማን አማን እብለከ አመ ወሬዛ አንተ ለሊከ ትቀንት ሐቌከ ወተሐውር ኀበ ፈቀድከ ፡ ወአመሰ ልህቀ ታነሥእ እደዊከ ወባዕድ ያቀንተከ ሐቌከ ወይወስደከ ኀበ ኢፈቀድከ ።

፲፱ ወዘንተ ይቤሎ እንዘ ይኤምር በአይ ሞት ሀለዎ ይሰብሖ ለእግዚአብሔር ወዘንተ ብሂሎ ይቤሎ ትልወኒ ።

፳ ወተመይጠ ጴጥሮስ ርእዮ ለዝኩ ረድእ ዘያፈቅሮ እግዚእ ኢየሱስ እንዘ ይተልዎ ወውእቱ ረድእ ዘረፈቀ ዲበ እንግድዓሁ ለእግዚእ ኢየሱስ እንዘ ይዴረሩ ወዘይቤሎ እግዚኦ መኑ ውእቱ ዘያገብእከ ።

፳፩ ወኪያሁ ርእዮ ጴጥሮስ ይቤሎ ለእግዚእ ኢየሱስ እግዚኦ ዝኬ እፎ ።

፳፪ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ እመኬ ፈቀድኩ የሀሉ እስከ ሶበ እመጽእ ሚ ላዕሌከ ወአንተሰ ትልወኒ ።

፳፫ ወወፅአ ዝንቱ ነገር በኀበ አኀው ከመ ውእቱ ረድእ ኢይመውት ፡ ወባሕቱ እግዚእ ኢየሱስ ኢይቤሎ ኢይመውት አላ ይቤ እመ ፈቀድኩ የሀሉ እስከ ሶበ እመጽእ ሚ ላዕሌከ ።

፳፬ ወዝንቱ ውእቱ ረድእ ዘኮነ ሰማዕተ በእንተዝ ወዘሂ ጸሐፈ በእንቲአሁ ዘንተ ወንሕነ ነአምር ከመ ጽድቅ ውእቱ ስምዑ ።

፳፭ ወዘንተ ገብረ እግዚእ ኢየሱስ ወበ በዕዳትኒ ብዙኃት ግብራት ዘገብረ እግዚእ ኢየሱስ ወሶበ ተጽሕፈ ኵሉ በበአሐዱ እምኢያገመሮ ዓለም ጥቀ ለመጻሕፍቲሁ ዘተጽሕፈ ።

መልአ ጽሕፈተ ብሥራቱ ለዮሐንስ ሐዋርያ ወልደ ዘብዴዎስ አሐዱ እምዐሠርቱ ወክልኤቱ ሐዋርያት ፡ ዘጸሐፎ በልሳነ ዮናናውያን ለሰብአ ሀገረ ኤፌሶን እምድኅረ ዕርገቱ ለእግዚእነ በሥጋ ውስተ ሰማይ በ፴ ዓመት ወ፯ቱ ዓመተ መንግሥቱ ለኔሮን ቄሣር ።

ወስብሐት ለእግዚአብሔር ፡

አ ሜ ን ።

እሱም አዎን አቤቱ ! እኔ እንደምወድህ አንተ ታውቃለህ አለው ፡ ጠቦቶቼን ጠብቅ አለው ። ዕብ ፲፫ ፳ ፩ ጴጥ ፭ ፡ ፪ - ፬ ።

ሦስተኛም የዮና ልጅ ስምዖን ! ትወደኛለህን? አለው ጴጥሮስም ሦስት ጊዜ ትወደኛለህ? ስላለው አዘነ ፡ አቤቱ ! አንተ ሁሉን ታውቃለህ እኔም እንደምወድህ አንተ ታውቃለህ አለው ፡ እንኪያስ በጎቼን ጠብቅ አለው ። ምዕ ፲፫ ፡ ፴፰ ። ፲፯

እውነት እውነት እልሃለሁ አንተ ጐልማሳ ሳለህ በገዛ እጅህ ወገብህን ታጥቀህ ወደ ወደድከውም ትሄዳለህ ፡ በሽመገልክ ጊዜ ግን እጅህን ታነሣና ወገብህን ሌላ ያስታጥቅሃል ወደ ማትወደውም ይወስድሃል ። ምዕ ፲፫ ፡ ፴፮ ። ፲፰

በምን ሞት እግዚአብሔርን ያገለግለው ዘንድ እንዳለው ሲያመለክተው ይህን ተናገረ ፡ ይህንም ተናግሮ ተከተለኝ አለው ። ፲፱

ጴጥሮስም መለስ ብሎ ያን ጌታ ኢየሱስ ይወደው የነበረውን ደቀ መዝሙር ሲከተለው አየ ፡ ያም ደቀ መዝሙር ራት ሲበሉ በጌታ ኢየሱስ አጠገብ የተቀመጠውና አቤቱ የሚያስይዝህ ማነው ? ያለው ነው ። ምዕ ፲፫ ፡ ፳፫ ። ፳

ጴጥሮስም እርሱን አይቶ ጌታ ኢየሱስን አቤቱ ! ይህስ እንዴት ይሁን ? አለው ። ፳፩

ጌታ ኢየሱስም እስከመጣ ድረስ ይኖር ዘንድ ብወደድኩ አንተ ምን አለህ ? አንተስ ተከተለኝ አለው ። ማቴ ፲፮ ፡ ፳፯ ። ፩ ቆሮ ፬ ፡ ፭ ። ራ ዮሐ ፪ ፡ ፳፭ ። ፳፪

ያም ደቀ መዝሙር እንደማይሞት ይህ ነገር በሐዋርያት ዘንድ ተረጋገጠ ፡ ጌታ ኢየሱስ ግን እስከመጣ ይኖር ዘንድ ከወደድኩ አንተ ምን አለህ? አለ እንጂ አይሞትም አላለም ። ፳፫

ስለዚህ ነገር ምስክር የሆነ ስለ ራሱም ይህን የጻፈ ይህ ደቀ መዝሙር ነው ፡ ምስክርነቱም እውነት እንደሆነ እኛ እናውቃለን ። ምዕ ፲ ፡ ፴፭ ። ራእ ዮሐ ፩ ፡ ፪ ። ፳፬

ጌታ ኢየሱስ ይህን አደረገ ፤ ጌታ ኢየሱስ የሠራቸው ሌሎች ሥራዎችም አሉ ፡ ሁሉ እያንዳንዱ ቢጻፍ ዓለም ባልቻለውም ነበር በመጻሕፍቶቹም የተጻፈው እጅግ ነው ። አሞጽ ፯ ፡ ፲ ። ምዕ ፳ ፡ ፴ ። ፳፭

ከዐሥራ ሁለቱ ሐዋርያት አንዱ የሆነው የዘብዴዎስ ልጅ ጌታችን በሥጋ ወደ ሰማይ ባረገ በሠላሳ ዘመን ፡ ኔሮን ቄሣር በነገሠ በሰባት ዓመት በዕርእ ቋንቋ ለኤፌሶን ሰዎች የጻፈው የሐዋርያ ዮሐንስ ወንጌል ጽሕፈት ተፈጸመ ።

ለእግዚአብሔር ምስጋና ይሁን ፡

አ ሜ ን ።

## ግብረ ሐዋርያት ፩

መጽሐፈ ግብረ ልኡካን ዝ ውእቱ ዜና ሐዋርያት ንጹሓን እምጊዜ ዕርገቱ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ዘጸሐፈ ሉቃስ ወንጌላዊ ወፈነዎ ኀበ ታኦፊላ ዘጸሐፈ ሎቱ ቀዳሚ ወንጌለ ።

ምዕራፍ ፩ ፤

ክፍል ፩ ፡ በእንተ አስተጋብኦ ዜና ሐዋርያት ።

፩ ቀዳሚ ጸሐፍኩ ለከ መጽሐፈ ኦ ታኦፊላ በዘኵሉ ግብር ዘአኀዘ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ይግበር ወይምሀር ።

፪ እስከ ዕለት እንተ ባቲ ዓርገ አዚዞ ለሐዋርያቲሁ ለእለ ኀረዮሙ በመንፈስ ቅዱስ ።

፫ እሉ እሙንቱ እለ አርአዮሙ ወከሠተ ሎሙ ርእሰ ሕያወ እምድኅረ ሞተ በተአምር ብዙኅ በአርብዓ ዕለት እንዘ ያስተርእዮሙ ወይዜንዎሙ ወይነግሮሙ በእንተ መንግሥተ እግዚአብሔር ።

ክፍል ፪ ፡ በእንተ ጥምቀት በመንፈስ ቅዱስ ።

፬ ወእንዘ ይመስሕ ምስሌሆሙ አዘዞሙ ኢይግኅሡ እም ኢየሩሳሌም አላ ይጽንሑ ተስፋሁ ለአብ ።

፭ ወይቤሎሙ ዮሐንስ አጥመቀ በማይ አንትሙሰ ታጠምቁ በመንፈስ ቅዱስ እስከ ኀዳጥ መዋዕል ዘኢኮነ ርኁቀ ።

ክፍል ፫ ፡ ተስእሎ በእንተ መንግሥተ እስራኤል ።

፮ ወእንዘ ጉቡአን እሙንቱ ተስእልዎ ወይቤልዎ እግዚኦ በዝኑ መዋዕል ታገብእ መንግሥተ ለደቂቀ እስራኤል ? ።

፯ ወአውሥኦሙ ወይቤሎሙ ኢኮነ ለክሙ ታእምሩ መዋዕለ ወአዝማነ ዘሠርዐ አብ በምኵናኑ ባሕቲቱ ።

፰ አላ ሰበ ይወርድ ላዕሌክሙ መንፈስ ቅዱስ ትነሥኡ ኃይለ ወትከውኑኒ ሰማዕትየ በኢየሩሳሌም ወበኵሉ ይሁዳ ወሰማርያ ወእስከ አጽናፈ ምድር ።

ክፍል ፬ ፡ በእንተ ዕርገት ።

፱ ወዘንተ እንዘ ይብሎሙ ተለዐለ ወነሥኦቶ ደመና ወዐርገ ሰማየ እንዘ እሙንቱ ይኔጽሩ ኀቤሁ፡ ወተሠወረ እምአዕይንቲሆሙ ።

## የሐዋርያት ሥራ ፩

የሐዋርያትን ሥራ የሚናገር መጽሐፍ ፡ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ካረገበት ጊዜ ጀምሮ የተሠራውን ወንጌላዊ ሉቃስ ወንጌል ጽፎ ለላከለት ለታኦፊላ መጀመርያ የጻፈለት የንጹሐን ሐዋርያት ዜና ይህ ነው ።

ምዕራፍ ፩ ፤

ክፍል ፩ ፡ የሐዋርያትን ዜና ስለ መሰብሰብ ።

ታኦፊላ ሆይ ! ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ሊያደር ፩
ገው ሊያስተምረው የጀመረውን ሥራ ከሁሉ አስቀ
ድሜ በመጽሐፍ ጽፌልሃለሁ ። ሉቃ ፩ ፡ ፫ ።
በመንፈስ ቅዱስ ለመረጣቸው ለሐዋርያቱ ትእዛዙን ፪
ሰጥቶ እስከ ዐረገበት ቀን ድረስ ያለውን ። ፩ ጢሞ
፫ ፡ ፲፮ ። ዕብ ፩ ፡ ፪-፫ ።
ብዙ ተአምራትን በማሳየት ከሞተ በኋላ ፡ በአርባው ፫
ቀን ተገልጦ ስለ እግዚአብሔር መንግሥት ነግሮ
አስተምሮ ሕያው ራሱን የገለጠላቸው እነዚህ ናቸው።
ሉቃ ፲፯ ፡ ፳-፳፩ ። ሮሜ ፲፬ ፡ ፲፯ ። ፩ ቆሮ ፲፭ ፡ ፭ ።

ክፍል ፪ ፡ በመንፈስ ቅዱስ ስለ ማጥመቅ ።

ከእነርሱ ጋር ምሳ ሲበላም ፡ የአብን ተስፋ እንዲ ፬
ጠብቁ እንጂ ከኢየሩሳሌም እንዳይወጡ አዘዛ
ቸው ። ዮሐ ፲፭ ፡ ፳፮ ። ሉቃ ፳፬ ፡ ፵፱ ።
ዮሐንስ በውኃ አጠመቀ ፡ እናንተ ግን ሩቅ እስከ ፭
ልሆን እስከ ጥቂት ቀን ድረስ በመንፈስ ቅዱስ ታጠ
ምቃላችሁ ። ኢዩ ፪ ፡ ፳፰-፳፱ ። ምሳ ፲፩ ፡ ፲፯ ።
፲፫ ፡ ፴፩ ። ማቴ ፫ ፡ ፲፩ ።

ክፍል ፫ ፡ ስለ እስራኤል መንግሥት ጥያቄ ።

እነርሱም ተሰብስበው ሳሉ አቤቱ ! በዚህ ዘመን የእስ ፮
ራኤልን መንግሥት ትመልሳለህን? ብለው ጠየቁት ።
ሉቃ ፳፬ ፡ ፳፩ ።
አብ በገዛ ሥልጣኑ የወሰነውን ቀኑን ዘመኑን ልታ ፯
ውቁ አልተፈቀደላችሁም ብሎ መለሰላቸው ። ዘዳ
፳፱ ፡ ፳፱ ። ፩ ተሰ ፭ ፡ ፩ ።
መንፈስ ቅዱስ በናንተ ላይ በወረደ ጊዜ ኀይልን ፰
ታገኛላችሁ ፡ በኢየሩሳሌም በይሁዳ በሰማርያ እስከ
ምድር ዳርቻ ድረስም ምስክሮች ትሆኑኛላችሁ አንጂ።

ክፍል ፬ ፡ ስለ ዕርገት ።

ይህንንም እየነገራቸው ከፍ ከፍ አለ ደመናም ተቀበ ፱
ለችው ፡ እነሱ እያዩትም ወደ ሰማይ ዐረገ ፡ ከዓይና
ቸውም ተሠወረ ። ማር ፲፮ ፡ ፲፱ ። ሉቃ ፳፬ ፡ ፶፩ ።
ዮሐ ፯ ፡ ፴፪ ።

፲ ወአስተርአይዎሙ ክልኤቱ አደው ወቆሙ ኀቤ
ሆሙ ወይለብሱ ፀዐዳ ።
፲፩ ወይቤልዎሙ አንትሙ ሰብአ ገሊላ ምንትኑ ቆም
ክሙ ትርአዩ ሰማየ ዝ ውእቱ ኢየሱስ ዘዐርገ እም
ኀቤክሙ ውስተ ሰማይ ፡ ወከማሁ ከዐበ ይመጽእ
በከመ ርኢክምዎ የዐርግ ሰማየ ።
፲፪ ወእምዝ ተሠውጡ ኢየሩሳሌም እምደብረ ዘይት
ዘእቱት እምኢየሩሳሌም መጠነ ምርዋፀ ብእሲ እንተ
ይእቲ መንገደ ቀዳም ።

## ክፍል ፫ ፡ በእንተ ጸሎተ ማኅበር ።

፲፫ ወበጺሖሙ ማኅደሮሙ ኀበ ይነብሩ ጽርሐ ዓርጉ
ጴጥሮስ ወዮሐንስ ወያዕቆብ ወእንድርያስ ወፊልጶስ
ወቶማስ ወማቴዎስ ወበርተሎሜዎስ ወያዕቆብ ወልደ
እልፍዮስ ወስምዖን ቀናኢ ወይሁዳ ወልደ ዮሴፍ ።

፲፬ እሉ ኵሎሙ ይፀመዱ ጸሎተ ኅቡረ ምስለ አንስት
ወማርያም እሙ ለኢየሱስ ወአኀዊሁ ።

## ክፍል ፬ ፡ በእንተ ኅርየት ።

፲፭ ወውእተ አሚረ ተንሥአ ጴጥሮስ ወቆመ ማእከለ
አኀዊሁ ወይቤሎሙ እንዘ ሀለዉ ህየ ሰብእ ወየአ
ክሉ ምእተ ወዕሥራ ።
፲፮ ስምዑ አ እኀዊነ አማን ሀለዎ ይብጻሕ ቃለ መጽሐፍ
ዘይቤ መንፈስ ቅዱስ በአፈ ዳዊት በእንተ ይሁዳ
ዘውእቱ ከነሙ መርሐ ለእለ አኀዝዎ ለእግዚእ
ኢየሱስ ።
፲፯ እንዘ ኁሉቍ ውእቱ ምስሌነ ወከፈሎ ዘንተ
መልእክተ ።
፲፰ ወእምዝ ተሣየጠ ዓፀደ በፀሰበ ዓመፃሁ ወተነጽሐ
ላዕለ ምድር በገጹ ወተሠጥቀ ገበሁ ወተክዕወ ኵሉ
አማዑቲሁ ።

፲፱ ወተሰምዐ ነገሩ በኀበ ኵሎሙ እለ ይነብሩ በኢየሩ
ሳሌም ወተሰምየ ዓፀዱ ዘተሣየጠ በዐሥቡ ሰመይዎ
በነገሮሙ ሐቅለ ድማህ ገራህተ ደም ብሂል ።
፳ በከመ ይቤ መጽሐፈ መዝሙር ለትኩን ሀገሩ በድወ
ወአልቦ ዘይነብር ውስቴታ ፡ ወሢመቶሂ ይንሣእ
በዕድ ።
፳፩ ወይደሉ ለአሐዱ እምእሉ እደው እለ ነበሩ ምስ
ሌነ ዘንተ ኵሎ መዋዕለ ዘቦአ ወወፅአ በኀቤነ እግ
ዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ።
፳፪ እንዘ እምጥምቀተ ዮሐንስ እስከ አመ ዓርገ እምኀ
ቤነ ከመ ይኩን ውእቱ ምስሌነ ስምዐ ተንሥኦቱ ።



ሁለት ሰዎችም ነጫጭ ልብስ ለብሰው ባጠገባቸው ፲
ቁመው ታዩአቸው ። ሉቃ ፳፬ ፡ ፬ ።
እናንት የገሊላ ሰዎች! ለምን ወደላይ እያያችሁ ፲፩
ቆማችኋል ? ከእናንት ወደ ሰማይ ያረገው ይህ ኢየ
ሱስ ነው ፡ እንዲሁም ወደ ሰማይ ሲያርግ እንዳያ
ችሁት ዳግመኛ ይመጣል አሏቸው ። ሉቃ ፳፩ ፡ ፳፯ ።
ከዚህ በኋላ ያንዳፍታ ሩጫ ያህል ከኢየሩሳሌም ፲፪
ራቅ ካለችው ከደብረ ዘይት ወደ ኢየሩሳሌም ተመ
ለሱ ፡ ያንዳፍታ ሩጫ ማለትም የቀዳሚ መንገድ
ታህል ናት ። ዘካ ፲፬ ፡ ፬ ። ሉቃ ፳፬ ፡ ፶ ። ዮሐ ፲፩ ፡ ፲፰ ።

## ክፍል ፫ ፡ ስለ ማኅበር ጸሎት ።

ወደ ማደሪያቸውም በደረሱ ጊዜ ጴጥሮስ፡ ዮሐንስ፡ ፲፫
ያዕቆብ፡ እንድርያስ፡ ፊልጶስ፡ ቶማስ፡ ማቴዎስ፡ በር
ተሎሚዎስ፡ የእልፍዮስ ልጅ ያዕቆብ፡ ቀናተኛው
ስምዖንና የዮሴፍ ልጅ ይሁዳ ወደሚኖሩበት ሰገነት
ወጡ ። ማቴ ፲ ፡ ፪ ። ሉቃ ፮ ፡ ፲፫ - ፲፭ ።
እነዚህ ሁሉ ከሴቶች ጋር በአንድነት ጸሎት ያደርጉ ፲፬
ነበር ፡ የኢየሱስ እናት ማርያምና ወንድሞቹም አብ
ረው ነበሩ ። ምዕ ፪ ፡ ፩ ። ሉቃ ፳፫ ፡ ፵፱ ።

## ክፍል ፬ ፡ ስለ ምርጫ ።

ያን ጊዜም ጴጥሮስ ተነሥቶ በወንድሞቹ መካከል ፲፭
ቆመ ፡ ሰዎች ከዚያ ሳሉም እንዲህ አላቸው ፡ መቶ
ሃያም ያህሉ ነበር ። ራእ ፫ ፡ ፬ ።
ወንድሞቻችን! ስሙ መንፈስ ቅዱስ በዳዊት አድሮ ፲፮
የተናገረው ይፈጸም ዘንድ አለው ፡ ይኸውም ጌታ
ኢየሱስን ለያዙት መሪ የሆነው ነው ። መዝ ፵፩ ፡ ፲ ።

ከኛ ጋር የተቈጠረና ይህንንም አገልግሎት ያደለው ፲፯
ሲሆን ። ሉቃ ፮ ፡ ፲፮ ።
ከዚህም በኋላ በዐመፅ ዋጋው በታን ገዛ ፡ ከምድር ፲፰
በግንባሩም ፍግም ብሎ ወድቆ ገላ ተቀዶ ፡ የ
ውስጥ አንጀቱ ሁሉ ተዘረገፈ ። መዝ ፶፭ ፡ ፳፫ ።
ማቴ ፳፯ ፫ - ፲ ። ፪ ጴጥ ፪ ፡ ፲፭ ።
በኢየሩሳሌም በሚኖሩት ሁሉ ዜናው ተሰማ ፡ በዓ ፲፱
መፅ ዋጋ የገዛውን በታ በቋንቋቸው "ሐቅለ ድማህ"
አሉት ፡ ይኸውም የደም ምድር ማለት ነው ።
የመዝሙር መጽሐፍ እንደ ተናገረ "አገሩ ምድረ በዳ ፳
ትሁን ፡ በውስጧም የሚኖር አይኑር ሹመቱንም
ሌላ ይውሰዳት" ። መዝ ፷፱ ፡ ፳፭ ። ፻፱ ፡ ፰ ።
እንግዲህ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በወጣበት በገ ፳፩
ባበት ይህን ያህል ዘመን ሁሉ አብረውን ከነበሩት
ከነዚህ ሰዎች ለአንዱ ሊሆን ይገባል ። ዮሐ ፲፭ ፡ ፳፯ ።
ከዮሐንስ ጥምቀት ጀምሮ ከእኛ ተለይቶ እስከ ዐረገ ፳፪
በት ድረስ እሱም አብሮን የትንሣኤው ምስክር
ይሆን ዘንድ ። ዕብ ፪ ፡ ፫ ።

፳፫ ወአቀሙ ክልኤተ ዮሴፍሃ ዘተሰምየ በርናባስ ዘይ
ብልዎ ኢዮስጦስ ወማትያስሃ ።
፳፬ ወጸለዩ ወይቤሉ አንተ እግዚኦ ማእምረ ኵሉ ልብ
አርኢ አሐደ እምእሉ ክልኤተ ዘኀረይከ ።
፳፭ ዘይነሥኦ ለመልእክተ ዛቲ ሢመት ሐዋርያት ዘኀ
ደጋ ይሁዳ ይሑር ብሔሮ ።
፳፮ ወአስተዓፀውዎሙ ወበጽሐ ዕፃ ዲበ ማትያስ ወተ
ኈለቈ ምስለ ዐሠርቱ ወአሐዱ ሐዋርያት ።

ምዕራፍ ፪ ፤

## ክፍል ፩ ፤ በእንተ ርደተ መንፈስ ቅዱስ ።

፩ ወአመ ተፈጸመ መዋዕለ ጰንጠቆስጤ እንዘ ሀለዉ
ኵሎሙ ኅቡረ አሐተኔ ።
፪ መጽአ ግብተ እምሰማይ ድምፅ ከመ ድምፀ ነፋስ
አውሎ ወመልአ ኵሎ ቤተ ኀበ ሀለዉ ይነብሩ ።
፫ ወአስተርአይዎሙ ልሳናት እሳት ክፉላት ከመ እሳት
ዘይትከፈል ወነበረ ዲበ ኵሎሙ ።
፬ ወተመልኡ ኵሎሙ መንፈሰ ኃይል ወአኀዙ ይንብቡ
ዘዘዚአሆሙ በነገረ ኵሉ በሐውርት በከመ ወሀቦሙ
መንፈስ ቅዱስ ይንብቡ ።

## ክፍል ፪ ፤ በእንተ አሕዛብ እለ መጽኡ ለበዓል ።

፭ ወሀለዉ በኢየሩሳሌም ሰብእ ኄራን አይሁድ ይነ
ብሩ እምኵሉ አሕዛብ ዘመትሕተ ሰማይ ።
፮ ወሰሚዖሙ ዘንተ ቃለ ተጋብኡ ኵሎሙ ድንጉፃኒ
ሆሙ እስመ ሰምዕዎሙ ይነብቡ ኵሎሙ በነገረ
በሐውርት ።
፯ ወደንገፁ ወአንከሩ ወይቤሉ አኮኑ ሰብአ ገሊላ እሉ
ኵሎሙ ።
፰ እፎኑ እንከ ንሰምዖሙ ይነብቡ በነገረ ኵሉ በሐው
ርት እንዘ ፍጥረትነ ጳርቴ ወሜድ ወኢላሜጤ ።
፱ ወእለሂ ይነብሩ ማእከለ አፍላግ አይሁድ ወቀጳዶ
ቅያ ወፋንጦስ ወእስያ ።
፲ ወፍርግያ ወጵንፍልያ ወግብፅ ወደወለ ልብያ ወእ
ለሂ እምቀርኔን ወእለሂ መጽኡ እምሮሜ አይሁድ
ፈላስያን ።
፲፩ ወእለሂ እምቀርጤስ ወዓረብ ወናሁ ንሰምዖሙ ይነ
ብቡ በነገረ በሐውርቲነ ዕበያቲሁ ለእግዚአብሔር ።
፲፪ ወደንገፁ ኵሎሙ ወኃጥኡ ዘይብሉ ወዘይነብቡ
ወተባሀሉ በበይናቲሆሙ ምንትኑ እንጋ ዝ ።
፲፫ ወመንፈቆሙሰ ሰሐቅዎሙ ወይቤሉ እሉሰ ፃዕፈ
ጸግቡ ወሰክሩ ።



ኢዮስጦስ የሚሉት በርናባስ የተባለው ዮሴፍንና ፳፫
ማትያስን ሁለቱን ሰዎች አቆሙ ።
አቤቱ ! ልቡናን ሁሉ የምታውቅ አንተ ከእነዚህ ከሁ ፳፬
ለቱ የመረጥከውን አንዱን ግለጥ ። መዝ ፯ ፡ ፲ ።
ዮሐ ፪ ፡ ፳፬ ። ዕብ ፬ ፡ ፲፫ ። ራእ ዮሐ ፪ ፡ ፳፫ ።
ይሁዳ ወደ አገሩ ይሄድ ዘንድ የተዋትን ይህችን ፳፭
የሐዋርያት የሹመት መልእክት የሚቀበላትን ።
ዕጣ አጣጣሏቸው ዕጣውም በማትያስ ላይ ወጣና ፳፮
ከዐሥራ አንዱ ሐዋርያትም ተቈጠረ ።

ምዕራፍ ፪ ፤

## ክፍል ፩ ፡ ስለ መንፈስ ቅዱስ መውረድ ።

የጰንጠቆስጤ ቀንም በተፈጸመ ጊዜ ሁሉም በአን ፩
ድነት ተሰብስበው ሳሉ ። ዘሌ ፳፫ ፡ ፲፭ - ፳፪ ። ዘዳግ
፲፮ ፡ ፬ ። ምዕ ፩ ፡ ፲፬ ።
ድንገትም ከሰማይ እንደ አውሎ ነፋስ ድምፅ ያለ ፪
ድምፅ መጥቶ የነበሩበትን ቤት መላው ። ምዕ ፬ ፡ ፴፩ ።
እየተጕረደ እንደሚሄድ እሳት የተከፋፈሉ የእሳት ፫
ላንቃዎች ታዩአቸው ፤ በሁሉም ላይ አረፈባቸው ።
ማቴ ፫ ፡ ፲፩ ።
ሁሉም የመንፈስን ኃይል ተመሉ ፤ ይናገሩ ዘንድ ፬
መንፈስ ቅዱስ እንደ ዓደላቸው መጠን እየራሳቸው
በሀገሩ ሁሉ ቋንቋ ይናገሩ ጀመሩ ። ምዕ ፲ ፡ ፵፬ ።
ሉቃ ፬ ፡ ፩ ። ዮሐ ፲፬ ፡ ፳፮ ።

## ክፍል ፪ ፡ ለበዓል ስለ መጡ አሕዛብ ።

ከሰማይ በታች ካሉ አሕዛብ ሁሉ የሚኖሩ ደጋግ ፭
አይሁድ ሰዎች በኢየሩሳሌም ነበሩ ። ዘፀ ፳፫ ፡ ፲፯ ።
ምዕ ፲፫ ፡ ፳፮ ።
ይህን ቃል ሲናገሩ ሰምተው ሁሉም ደንግጠው ፮
ተሰበሰቡ ፤ ሁሉ በያገራቸው ቋንቋ ሲናገሩ ሰምተ
ዋቸዋልና ።
ደንግጠውም እነዚህ ሁሉ የገሊላ ሰዎች አይደሉ ፯
ምን ?! ብለው አደነቁ ።
እንግዲህ ትውልዳችን ጳርቴ ሜድ ኤላሜጤ ሲሆን ፰
በየሀገራችን ቋንቋ ሲናገሩ እንዴት እንሰማቸዋለን ! ።
በቀጶዶቅያ በፋንጦስ በእስያ በወንዝ መካከል የሚ ፱
ኖሩ አይሁድም ነበሩ ። ፩ ጴጥ ፩ ፡ ፩ ።
ከፍርግያ ከጵንፍልያ ከግብፅ ከሊብያ አውራጃ ከቀ ፲
ርኔን ከሮሜም የመጡ ስደተኞች ነበሩ ። ዘፀ ፲፪ ፡
፵፰ ። ኢሳ ፶፮ ፡ ፮ ።
ከቀርጤስና ከዓረብም የመጡ ነበሩ ፤ እነሆ የእግዚአ ፲፩
ብሔርን ጌትነት በየሀገራችን ቋንቋ ሲናገሩ እንሰማ
ቸዋለን ።
ሁሉም ደንግጠው የሚሉትንና የሚናገሩትን አጡ ፤ ፲፪
እርስ በርሳቸውም ይህ ነገር ምን ይሆን ! ተባባሉ ።
እኩሌቶቹ ግን እነዚህስ ጉሽ ጠጅ ጠግበው ሰክ ፲፫
ረው ነው ብለው ሳቁባቸው ።

## ክፍል ፱ ፡ በእንተ ስብከተ ጴጥሮስ ቀዳሚት ።

፲፬ ወቆመ ጴጥሮስ ምስለ ዐሠርቱ ወአሐዱ ወከልሐ በቃሉ ወይቤ አንትሙ ሰብአ ይሁዳ ወእለሂ ትነብሩ ኢየሩሳሌም ኵልክሙ አእምሩ ዘንተ ወስምዑኒ ቃልየ ።
፲፭ እኮ ከመ ትትሔዘብዎሙ አንትሙ ስኩራን እሙንቱ እንዘ ትብሉ እስመ ነግህ ብሔሩ ወሰቤሁ ሠለስቱ ሰዓት ።
፲፮ አላ ዝ ውእቱ ዘይቤ ኢዮኤል ነቢይ ።
፲፯ ወይከውን እምድኅረዝ መዋዕል ይቤ እግዚአብሔር እሰውጥ እምነ መንፈስየ ዲበ ኵሉ ዘሥጋ ወይትኔበዩ ደቂቅክሙ ወአዋልዲክሙ ወወራዙቲክሙ ራእየ ይሬእዩ ወሊቃውንቲክሙ ሕልመ የሐልሙ ።
፲፰ ወላዕለ አግብርትየ ወአእማትየ እክዑ እምነ መንፈስየ ፡ ወይእተ አሚረ ይትኔበዩ ።
፲፱ ወእሁብ ትእምርተ በሰማይ በላዕሉ ወመንክረ በምድር በታሕቱ ደመ ወእሳተ ወጢሰ ።
፳ ፀሐይኒ ይጽልም ወወርኅኒ ደመ ይከውን ።
፳፩ ዘእንበለ ትብጻሕ ዕለተ እግዚአብሔር ዐባይ ወግርምት ፡ ወኵሉ ዘጸውዐ ስመ እግዚአብሔር ይድኅን ።

## ክፍል ፲ ፡ በእንተ ብእሲ

## ዘአርአየ እግዚአብሔር ለሕዝቡ ።

፳፪ ስምዑ ሰብአ እስራኤል ዘንተ ነገረ ኢየሱስ ናዝራዊ ብእሲ ዘአርአየክሙ እግዚአብሔር በኃይል ወበተአምር ወበመንክር ዘገብረ እግዚአብሔር በእደዊሁ በማእከሌክሙ ዘከመ ርኢክምዎ ።
፳፫ በሥርዓተ ምክሩ ወአእምሮቱ ለእግዚአብሔር መጠውክምዎ ውስተ እደ ኃጥኣን ወሰቀልክምዎ ወቀተልክምዎ ።
፳፬ ወእግዚአብሔር አንሥኦ እሙታን ፈቲሖ ማእሰሪሁ ለሞት እስመ ኢይክል እኂዞቶ ሞት ።
፳፭ ወዳዊትኒ ይቤ በእንቲአሁ ዘልፈ እሬእዮ ለእግዚአብሔር ቅድሜየ ውእቱ በኵሉ ጊዜ ፡ እስመ በየማንየ ውእቱ ከመ ኢይትሀወክ ።
፳፮ ወበእንተዝ ተፈሥሐ ልብየ ወተኃሥየ ልሳንየ ፡ ወዓዲ በተስፋሁ ኀደረ ሥጋየ ።



## ክፍል ፱ ፡ ስለ መጀመሪያይቱ የጴጥሮስ ስብከት ።

ጴጥሮስም ከዐሥራ አንዱ ጋር ቆሞ ድምፁን ከፍ ፲፬
አድርጎ እንዲህ አለ ፡ እናንት የይሁዳ ሰዎች በኢየ
ሩሳሌም የምትኖሩ ሁሉ ይህን ዕወቁ ቃሌንም ስሙኝ ።
ሰክረዋል እያላችሁ እናንተ እንደምትጠረጥሩአ ፲፭
ቸው አይደሉም ፡ ጊዜው ማለዳ ነውና እልፍ ቢልም
ሦስት ሰዓት ነውና ።
ይህ ነቢዩ ኢዩኤል የተናገረው ነገር ነው እንጂ ። ፲፮
ኢዩ ፪ ፡ ፳፰ ።
እግዚአብሔር እንዲህ አለ ፡ ከዚህ ዘመን በኋላ እን ፲፯
ዲህ ይሆናል ፡ ሥጋ በለበሰ ሁሉ መንፈሴን አሳድራ
ለሁ ፡ ሴቶች ልጆቻችሁ ትንቢት ይናገራሉ ፡ ጕልማሶ
ቻችሁ ራእይ ያያሉ ሊቃውንቶቻችሁም ሕልም ያል
ማሉ ። ምዕ ፳፩ ፡ ፱ ። ኢሳ ፵፬ ፡ ፫ ። ሕዝ ፲፩ ፡ ፲፱ ።
ኢዩ ፪ ፡ ፳፰ ። ዘካ ፲፪ ፡ ፲ ። ዮሐ ፯ ፡ ፴፰ - ፴፱ ።
በወንዶች በሴቶች ባሮቼ ላይ መንፈሴን አሳድራለሁ ፲፰
ያን ጊዜም ትንቢት ይናገራሉ ።
በላይ በሰማይም ምልክት አሳያለሁ በታች በምድ ፲፱
ርም ድንቅ ነገር አደርጋለሁ ፡ ደም ይፈሳል ቃጠሎ
ይሆናል ጢስ በገዞ ይታያል ። ኢዩ ፪ ፡ ፳፱ - ፴ ።
ፀሐይ ይጨልማል ጨረቃም ደም ይሆናል ። ኢሳ ፳
፲፫ ፡ ፲ ። ሕዝ ፴፪ ፡ ፯ ። ማቴ ፳፬ ፡ ፳፱ ። ራዮ ፯ ፡ ፪ ።
ታላቂቱና የምታስፈራዪቱ የእግዚአብሔር ቀን ሳት ፳፩
ደርስ የእግዚአብሔር ስም የጠራ ሰው ሁሉ ይድ
ናል ። ሮሜ ፲ ፡ ፲፫ ።

## ክፍል ፲ ፡ እግዚአብሔር ለሕዝቡ

## ስለ ገለጠው ሰው ።

የእስራኤል ሰዎች ! ይህን ነገር ስሙ ፡ የናዝሬቱ ኢየ ፳፪
ሱስ እንደ አያችሁት በመካከላችሁ እግዚአብሔር
በእጁ ባደረገው በከሀሊነቱ በተአምራቱ በድንቅ
ሥራው እግዚአብሔር የገለጠላችሁ ሰው ነው ።
ምዕ ፲ ፡ ፴፰ ።
እግዚአብሔር ዐውቆ መክሮ በሠራው ሥርዓት አሳ ፳፫
ልፋችሁ በኃጥአን እጅ ሰጣችሁትና ሰቀላችሁት ገደ
ላችሁትም ። ሉቃ ፳፬ ፡ ፵፬ ። ምዕ ፬ ፡ ፳፰ ።
እግዚአብሔር የሞትን ማሠሪያ ፈትቶ ከሙታን ለይቶ ፳፬
አስነሣው ፡ ሞት ሊያስቀረው አይችልምና ። ምዕ ፫ ፡
፲፭ ። ፩ ቆሮ ፯ ፡ ፲፬ ። ፩ ጴጥ ፩ ፡ ፩ ።
ዳዊትም ስለ እርሱ እንዲህ አለ "እግዚአብሔርን ዘወ ፳፭
ትር አየዋለሁ ፡ ሁልጊዜም በፊቴ ነው እንዳልታወክ
በቀኜ ነውና" ። መዝ ፲፮ ፡ ፲ ።
ስለዚህ ልቤ ደስ አለው ፡ አንደበቴም ደስታ መላው ፳፮
ዳግመኛም በተስፋው ሥጋዬ ጸና ።

፳፯ እስመ ኢተኃድጋ ውስተ ሲኦል ለነፍስየ፥ ወኢት
ሁብ ለጻድቅከ ይርአይ ሙስና ።
፳፰ ወመራሕከኒ ፍኖተ ሕይወት ፥ ወአጽገብከኒ ኃሤተ
ምስለ ገጽከ፡ ወትፍሥሕት ውስተ የማንከ ለዝሉፉ ።

ክፍል ፲ወ፩፡ በእንተ ዳዊት ርእሰ አበው ።

፳፱ ታበውሑኒሁ እንከ አ ሰብእ እንግርክሙ ክሡተ
በእንተ ዳዊት ርእሰ አበው ከመሂ ሞተ ወተቀብረ
ወኀቤነ ሀሎ መቃብሪሁ እስከ ዮም ።

፴ እስመ ነቢይ ውእቱ ወአእመረ ከመ በመሐላ መሐለ
ሎቱ እግዚአብሔር ከመ እምፍሬ ከርሡ ያነብር
ዲበ መንበሩ ።
፴፩ አቅዲሙ አእሚሮ ነገረ ከመ ይትነሣእ ክርስቶስ
እሙታን ወከመ ኢትትኀደግ ውስተ ሲኦል ነፍስቱ
ወከመሂ ኢይሬእያ ለሙስና ።
፴፪ ሎቱ ለኢየሱስ አንሥኦ እግዚአብሔር ወንሕነ
ኵልነ ሰማዕቱ ።
፴፫ ወይእዜሰ ከመ በየማነ እግዚአብሔር ተለዐለ ነሢኦ
እምኀበ አቡሁ ዘአሰፈወ መንፈስ ቅዱስ ሦጠ ለዝ
ዘትሬእዩ ወዘትሰምዑ ።

፴፬ በኑ ዳዊት ዐርገ ሰማየ፥ ኢይቤኑ ለሊሁ ዳዊት
በመንፈስ ቅዱስ ።
፴፭ ይቤሎ እግዚእ ለእግዚእየ ንበር በየማንየ እስከ
አገብኦሙ ለጸላእትከ ታሕተ መከየደ እገሪከ ።
፴፮ ጥዩቀ እንከ ያእምሩ ኵሉ ቤተ እስራኤል ከመ
እግዚአኒ ወመሲሐኒ ረሰዮ እግዚአብሔር ለውእቱ
ኢየሱስ ክርስቶስ ዘአንትሙ ሰቀልክምዎ ።

፴፯ ወሰሚዖሙ ተከሥተ ልበሙ ወይቤልዎሙ ለጴጥ
ሮስ ወለቢፁ ሐዋርያት ምንተ ንግበር አኀዊነ ።

፴፰ ወይቤሎሙ ጴጥሮስ ነስሑ ወተጠመቁ ኵልክሙ
በስሙ ለኢየሱስ ክርስቶስ ወይትኃደግ ለክሙ ኃጢ
አትክሙ ወትነሥኡ ጸጋሁ ለመንፈስ ቅዱስ ።

፴፱ እስመ ለክሙ ውእቱ ተስፋ ወለውሉድክሙ ወለኵ
ሎሙ እለ ርኁቃን እለ ጸውዖሙ እግዚአብሔር
አምላክነ ።
፵ ወበዕደኒ ብዙኀ ነገረ ነገሮሙ ወገሠፆሙ ወይቤ
ሎሙ አድኅኑ ነፍሰክሙ እምዝ ዓለም እኩይ ።

ክፍል ፲ወ፪፡ በእንተ ጥንተ ማኅበረ ክርስቲያን።

፵፩ ወተወክፉ ቃሎ ወተጠምቁ ወተወሰኩ በይእቲ
ዕለት መጠነ ሠላሳ ምእት ነፍስ ።

ነፍሴን በሲኦል አትተዋትምና ጻድቅህንም ሙስና ፳፯
መቃብር እንዲያይ አታደርገውምና ።
የሕይወትን መንገድ መራኸኝ ከፊትህም ጋር ደስታን ፳፰
አጸገብከኝ፥ ደስታም ዘወትር በቀኝህ ይኖራል" ።

ክፍል ፲፩፥ ስለ አባቶች አለቃ ስለ ዳዊት ።

ሰዎች ሆይ! እንግዲህ እንደ ሞተ እንደ ተቀበረ፥ ፳፱
መቃብሩም እስከ ዛሬ ድረስ ከእኛ ዘንድ እንደ አለ
የአባቶች አለቃ የዳዊትን ገልጬ እንድነግራችሁ
ትፈቅዱልኛላችሁ? ። ፩ ነገ ፪ ፥ ፲። ምዕ ፲፫ ፥ ፴፮ ።
ነቢይ ነበርና ከአብራኩ የተገኘውን በዙፋኑ እንዲ ፴
ያነግሥለት እግዚአብሔር መሐላን እንደ ማለለት
ዐወቀ ። ፪ ሳሙ ፯ ፥ ፲፪-፲፫ ። መዝ ፻፴፪ ፥ ፲፩ ።
ክርስቶስ ከሙታን ተለይቶ እንደሚነሣ ነፍሱም በሲ ፴፩
ኦል እንደማትቀር ሙስና መቃብርን እንዳያይት ዳዊት
አስቀድሞ ዐውቆ ተናገረ ። መዝ ፲፯ ፥ ፲ ።
እርሱን ኢየሱስን እግዚአብሔር አስነሣው እኛ ሁላ ፴፪
ችንም ምስክሮቹ ነን ። ምዕ ፫ ፥ ፲፭ ።
አሁን ግን በእግዚአብሔር ዕሪና በተቀመጠ ጊዜ ፴፫
ለደቀ መዛሙርቱ እልክላችኋለሁ ያላቸውን መንፈስ
ቅዱስን ከአባቱ ገንዘብ አድርጎ ይህን የምታዩትን
የምትሰሙትን በኛ ላይ አሳደረው ። ምዕ ፭ ፥ ፴፩ ።
በውኑ ዳዊት ወደ ሰማይ ዐርጓል? እርሱ ራሱ ፴፬
ዳዊትስ በመንፈስ ቅዱስ እንዲህ አላለምን? ።
"ጌታ ጌታዬን ጠላቶችህን ከእግርህ በታች እስክጥላ ፴፭
ቸው ድረስ በቀኜ ተቀመጥ አለው"። መዝ ፻፲ ፥ ፩ ።
እንግዲህ የእስራኤል ወገኖች ሁሉ እናንተ የሰቀላ ፴፮
ችሁትን ኢየሱስ ክርስቶስን እግዚአብሔር ጌታም
ክርስቶስም እንዳደረገው በጕላ በተረዳ ይወቁ ።
ምዕ ፭ ፥ ፴፩ ። ፪ ተሰ ፩ ፥ ፯-፲ ።
ይህንን በሰሙ ጊዜ ልባቸው ተገለጠና ጴጥሮስንና ፴፯
ወንድሞቹ ሐዋርያትን ወንድሞቻችን! ምን እናድ
ርግ? አሏቸው ። ዘካ ፲፪፥ ፲። ሉቃ ፫ ፥ ፰ ። ምዕ ፲፯ ፥ ፴።
ጴጥሮስም እንዲህ አላቸው ተመለሱና ሁላችሁም ፴፰
በኢየሱስ ክርስቶስ ስም ተጠመቁ፥ ኃጢአታችሁ
ይሠረይላችኋል፥ የመንፈስ ቅዱስ ጸጋንም ታገኛ
ላችሁ ። ምዕ ፫ ፥ ፲፯ ። ሉቃ ፳፬ ፥ ፵፯ ። ፪ ቆሮ ፯ ፥ ፲ ።
ተስፋው ለእናንተና ለልጆቻችሁ ርቀው ለነበሩ እግ ፴፱
ዚአብሔር አምላካችን ለጠራቸው ሁሉ ነውና ።
ኢዩ ፫ ፥ ፳፰ ። ሮሚ ፱ ፥ ፰ ። ኤፌ ፪ ፥ ፲፫ ።
ሌላም ብዙ ነገር ነገራቸው ከዚህ ከክፉ ዓለምም ነፍ ፵
ሳችሁን አድኑ ብሎ መከራቸው ።

ክፍል ፲፪፥ ስለ ክርስቲያን ማኅበር አጀማመር ።

ቃሉንም ተቀብለው ተጠመቁ፥ በዚያችም ዕለት ፵፩
ሦስት ሺሕ ያህል ሰዎች ተጨመሩ ።

፵፪ ወነበሩ ይፀመዱ ትምህርተ ሐዋርያት ወኅቡረ ይባ
ርኩ ማእደ በውስተ ጸሎት ።
፵፫ ወፈርሆሙ ኵሉ ዘነፍስ ወብዙኅ ተአምር ወመንክር
ይከውን በእደዊሆሙ ለሐዋርያት ።
፵፬ ወኵሎሙ እለ አምኑ ኅቡረ ይነብሩ ፡ ወድሙር ኵሉ
ንዋዮሙ ።
፵፭ ወጥሪቶሙ ይሠይጡ ወይሁቡ ለነዳያን በከመ መፍ
ቅዱ ለለአሐዱ ።
፵፮ ወኵሎ አሚረ ይፀመዱ በአሐዱ ነፍስ ወበአሐዱ
ሕሊና ውስተ ቤተ መቅደስ ወይባርኩ ማእደ በው
ስተ ቤትኒ ይሴሰዩ ሲሳዮሙ በትፍሥሕት ወበየው
ሃተ ልብ ፡ ወየአኵቱ እግዚአብሔርሃ ።
፵፯ ወበሙ ሞገስ በኀበ ኵሉ ሕዝብ ፡ ወእንተ ጸብሐት
ይዌስክ እግዚአብሔር ዲቤሆሙ ለእለ የሐይዉ ።

ምዕራፍ ፫ ፤

ክፍል ፲ወ፫ ፡ በእንተ ተአምር ቀዳሚት
ዘኮነት በእደ ሐዋርያት ።

፩ ወዐርጉ ምኵራበ ጴጥሮስ ወዮሐንስ ጊዜ ተሱዓት
ለጸሎት ።
፪ ወሀሎ ፩ዱ ብእሲ ዘዕዉስ እገሪሁ ወተወልደ ከማሁ
እምከርሠ እሙ ፡ ወይፀውርዎ ኵሎ ዕለተ ወያነብርዎ
ኆኅተ ምኵራብ እንተ ስማ አርያ ከመ ይስአል ምጽ
ዋተ እምኀበ እለ ይበውኡ ምኵራበ ።
፫ ወርእዮሙ ለጴጥሮስ ወለዮሐንስ ይበውኡ ምኵራበ
ወሰአሎሙ የሀብዎ ምጽዋተ ።
፬ ወተመይጥዎ ጴጥሮስ ወዮሐንስ ኀቤሁ ወይቤልዎ
ተመየጥ መንገሌነ ።
፭ ወነጸረ ኀቤሆሙ ወተሰፈወ የሀብዎ ምጽዋተ ።

፮ ወይቤሎ ጴጥሮስ ወርቀሰ ወብሩር አልብየ ወእምዘ
ብየሰ እሁበከ ናሁ በስሙ ለኢየሱስ ክርስቶስ ናዝ
ራዊ ተንሥእ ወሑር ።
፯ ወአኀዞ በእዴሁ ዘየማን ወአንሥኦ ወተንሥአ ሶቤሃ
ወጸንዐ እገሪሁ ወሐቌሁ ።

፰ ወሖረ ምስሌሆሙ እንዘ ይሤግር ወቦአ ምኵራበ
ወአእኰተ እግዚአብሔርሃ ።
፱ ወርእይዎ ኵሎሙ ሕዝብ እንዘ የሐውር ወየአኵት
እግዚአብሔርሃ ።
፲ ወአእመርዎ ከመ ውእቱ ዘይነብር በኆኅተ ምኵራብ
እንተ ስማ አርያ ወይስእል ወደንገፁ ወአንከሩ በእ
ንተ ተአምር ዘኮነ ላዕሌሁ ።
፲፩ ወእንዘ ይእኅዝዎ ጴጥሮስ ወዮሐንስ ይበውኡ ምኵ
ራበ ሮፁ ኵሉ ሕዝብ ኀቤሆሙ ኀበ ሐዋረ ሰሎሞን
ድንጉፃኒሆሙ ።

የሐዋርያትን ትምህርት ይከታተሉ ነበር ፡ በጸሎትም ፵፪
ማእድን በአንድነት ይባርኩ ነበር ። ምዕ ፳ ፡ ፯ ።
በሐዋርያትም እጅ ብዙ ተአምራትና ድንቅ ድንቅ ፵፫
ሥራ ይደረግ ነበርና ሰው ሁሉ ፈራቸው ።
ያመኑት ሁሉ በአንድነት ይኖሩ ነበር ፡ ገንዘባቸውም ፵፬
ሁሉ ያንድነት ነበር ። ምዕ ፬ ፡ ፴፪ ።
ጥሪታቸውንም እየሸጡ ለእያንዳንዱ እንደ መፍ ፵፭
ቅዱ ለነዳያን ይሰጡ ነበር ። ኢሳ ፶፰ ፡ ፯ ።
ሁልጊዜም አንድ አፍ ፡ አንድ ልብ ሆነው በቤተ ፵፮
መቅደስ ኢያገለገሉ ሥጋውን ደሙን ይቀበሉ ነበር ፡
በቤትም በቅንነት ደስ እያላቸው ምግባቸውን ይመ
ገቡ ነበር ፡ እግዚአብሔርንም ያመሰግኑ ነበር ።
በሕዝቡ ሁሉ ዘንድ መወደድ ነበራቸው ፡ በየቀኑም ፵፯
በሚድኑት ላይ እግዚአብሔር ይጨምር ነበር ።

ምዕራፍ ፫ ፤

ክፍል ፲፫ ፡ በሐዋርያት ሥልጣን
መጀመሪያ ስለ ተደረገችው ተአምር ።

ጴጥሮስና ዮሐንስ በዘጠኝ ሰዓት ለጸሎት ወደ ምኵ ፩
ራብ ወጡ ።
እግሩ ልምሾ የሆነ ከእናቱ ማኅፀን እንዲሁ ሆኖ ፪
የተወለደ አንድ ሰው ነበር ፡ ዘወትርም እየተሸከሙ
ወደ ምኵራብ ከሚገቡት ምጽዋት ይለምን ዘንድ
አርያ ከምትባል የምኵራብ ደጃፍ ያኖሩት ነበር ።
ጴጥሮስና ዮሐንስን ወደ ምኵራብ ሲገቡ አይቶ ፫
ምጽዋት ይሰጡት ዘንድ ለመናቸው ።
ጴጥሮስና ዮሐንስም ወደርሱ መለስ ብለው ወደኛ ፬
ዘወር በል አሉት ።
ምጽዋት ይሰጡት ዘንድም ተስፋ አድርጎ ወደነርሱ ፭
ተመለከተ ።
ጴጥሮስም ወርቅና ብር የለኝም ፡ ግን ካለኝ ልስጥህ ፮
እነሆ በናዝሬቱ በኢየሱስ ክርስቶስ ስም ተነሥተህ
ሂድ ። ምዕ ፲፬ ፡ ፱ - ፲ ።
ያን ጊዜም በቀኝ እጁ ይዞ አስነሣው ፡ እርሱም ፯
እግሩ ጸንቶለት ወገቡ ረትቶለት ወዲያው ተነሣ ።
ማቴ ፳ ፡ ፲፭ ።
እየተራመደም አብሮአቸው ሄደ ወደ ምኵራብ ገብ ፰
ቶም እግዚአብሔርን አመሰገነ ። ኢሳ ፴፭ ፡ ፮ ።
ሕዝቡ ሁሉ እግዚአብሔርን ሲያመሰግን በእግሩ ፱
ሲሄድ አዩት ።
እርሱ አርያ በምትባለው ምኵራብ ደጃፍ ተቀምጦ ፲
ይለምን የነበረው እንደሆነ ዐወቁና ደንግጠው በርሱ
ላይ የተደረገውን ተአምራት አደነቁ ።
ጴጥሮስና ዮሐንስም ይዘዉት ወደ ምኵራቡ ሲገቡ ፲፩
ሕዝቡ ሁሉ ደንግጠው ወደ ሰሎሞን በር ወደነርሱ
ሮጡ ። ዮሐ ፲ ፡ ፳፫ ። ምዕ ፭ ፡ ፲፪ ። ምዕ ፭ ፡ ፲፪ ።

ክፍል ፲ወ፩፡ በእንተ ዘተናገረ ጴጥሮስ ለሕዝብ ።

፲፪ ወሶበ ርእዮሙ ጴጥሮስ ለሕዝብ ይቤሎሙ እንትሙ ሰብእ እስራኤል ምንትኑ ታንክሩን ወምንትኑ ትኔጽሩነ ከመ ዘበኃይልነ ገበርናሁ ወከመ ዘበሥልጣንነ ረሰይናሁ እው እምኀበ ነፍሳቲነኑ አሕየውናሁ ለዝንቱ ከመ ይሑር በእገሪሁ ፡ አልቦኬ ።

፲፫ አላ አምላከ አብርሃም ወአምላከ ይስሐቅ ወአምላከ ያዕቆብ አምላከ አበዊነ ሰብሐ ለወልዱ ኢየሱስ ክርስቶስ ዘአንትሙ ሀለውክምዎ ወክሕድክምዎ በቅድመ ገጸ ጲላጦስ ፈቂዶ ውእቱ ያሕይዎ ለክሙ ።

፲፬ ወአንትሙሰ ክሕድክምዎ ለቅዱስ ወለጻድቅ ወሰአልክሙ ብእሴ ቀታሌ ነፍስ ያሕዩ ለክሙ ።

፲፭ ወለመልእክ ሕይወትሰ ቀተልክምዎ ፡ ወእግዚአብሔር አንሥኦ እሙታን ።

፲፮ ወነሕነ ኵልነ ሰማዕቱ ከመ በሃይማኖት ስሙ ለዝ ዘትሬእዩ ወተአምሩ አጽንዖ ወበሃይማኖት ዚአሁ ወሀበ ዘንተ ሕይወተ በቅድሜክሙ ።

፲፯ ወይእዜኒ አኃውየ አአምሩ ከመ በኢያእምሮ ገበርክምዎ ለዝ ከመ ገብሩ መላእክቲክሙ ።

፲፰ ወእግዚአብሔርሰ በከመ አቅደመ ነጊረ በአፈ ኵሎሙ ነቢያት ከመ ይትቀተል ክርስቶስ አብጽሐ ከማሁ ።

፲፱ ወይእዜኒ ነስሑ ወተጠመቁ ወይደመሰስ ለክሙ ኃጢአትክሙ ወይመጽእ ለክሙ መዋዕለ ሣህል እምቅድመ ገጹ ለእግዚአብሔር ።

፳ ወይፌንዎ ለክሙ ለኢየሱስ ክርስቶስ ዘአቅደመ ቀቢኦ ።

፳፩ ዘኪያሁ ይሴፈዉ ሰማያት ወምድር እስከ አመ ያስተራትዕ ኵሎ በከመ ነበበ እግዚአብሔር በአፈ ነቢያቲሁ ቅዱሳን እለ እምዓለም ።

፳፪ ሙሴሂ ይቤሎሙ ለአበዊነ ነቢየ ያነሥእ ለክሙ እግዚአብሔር አምላክነ እምአኃዊክሙ ዘከማየ ወሎቱ ስምዕዎ ኵሎ ዘይቤለክሙ ።

፳፫ ወኵላ ነፍስ እንተ ኢትሰምዖ ለውእቱ ነቢይ ለትሠረው እምሕዝብ ።

፳፬ ወኵሎሙ ነቢያት እለ እምአመ ሳሙኤል ነቢይ ወእለሂ እምድኅሬሁ ነገሩ ወአይድዑ በእንተ እላንቱ መዋዕል ።

፳፭ ወአንትሙ ውሉዶሙ ለነቢያት ወውሉደ ሥርዓት ዘሠርዓ እግዚአብሔር ለአበዊነ እስመ ይቤሎ ለአ

ክፍል ፲፩ ፡ ጴጥሮስ ለሕዝብ ስለ ተናገረው ነገር ።

ጴጥሮስም ሕዝቡን ባያቸው ጊዜ እንዲህ አላቸው ፲፪
እናንት የእስራኤል ሰዎች በኃይላችን እንደ አደረግ
ነው በሥልጣናችን እንደ ፈጸምነው አድርጋችሁ
ለምን ታዩናላችሁ ? ወይስ ይህ በእግሩ እንዲሄድ
በራሳችን ችሎታ አድነነዋልን ? የሰም ፡ ፪ ቆሮ ፫ ፡ ፭ ።
የአብርሃም አምላክ የይስሐቅ አምላክ የያዕቆብ አም ፲፫
ላክ የአባቶቻችን አምላክ እርሱ ሊያድንላችሁ ወዶ
ሳለ እናንተ በጲላጦስ ፊት የካዳችሁትን የወነጀላች
ሁትን ልጁ ኢየሱስ ክርስቶስን ገለጸው ። ምዕ ፭ ፡
፴ ። ዘፀ ፫ ፡ ፮ ። ፲፭ ፡ ፲፯ ። ምዕ ፪ ፡ ፳፫ ።
እናንተ ግን ቅዱሱን ጻድቁን ካዳችሁት ፡ ነፍሰ ገዳዩ ፲፬
ንም እንዲያድንላችሁ ለመናችሁ ። ማቴ ፳፯ ፡
፳ - ፳፭ ። ዮሐ ፯ ፡ ፴፱ ።
የሕይወትን ባለቤት ግን ገደላችሁት ፡ እግዚአብሔር ፲፭
ግን ከሙታን ለይቶ አስነሣው ። ምዕ ፪ ፡ ፳፬ - ፴፪ ።
፬ ፡ ፲ ። ሮሜ ፬ ፡ ፳፬ ። ፰ ፡ ፲፩ ።
ይህን የምታዩትን የምታውቁትን ስሙን በማመን ፲፯
እንደ አጸናው እርሱንም በማመን በፊታችሁ
ይህን ሕይወት እንደ ሰጠው እኛ ሁላችን ምስክሮች
ነን ። ማቴ ፱ ፡ ፳፪ ። ፩ ጴጥ ፩ ፡ ፳፩ ።
አሁንም ወንድሞቼ አለቆቻችሁ እንደ አደረጉ ይህን ፲፯
ባለማወቅ እንደ አደረጋችሁት ዕወቁ ። ሉቃ ፳፫ ፡
፴፬ ። ፩ ቆሮ ፪ ፡ ፰ ። ፩ ጢሞ ፩ ፡ ፲፫ ።
እግዚአብሔር ግን ክርስቶስ እንዲሞት በነቢያት ፲፰
ሁሉ አስቀድሞ እንደ ተናገረ እንዲሁ ፈጸመ ። ኢሳ
፶ ፡ ፯ ። ዳን ፱ ፡ ፳፯ ። ሉቃ ፳፬ ፡ ፳፯ ። ፩ ጴጥ ፩ ፡ ፲ ።
አሁንም እመኑ ተጠመቁ ኃጢአታችሁ ይሠረይላ ፲፱
ችኋል ከእግዚአብሔር ዘንድ የይቅርታ ዘመን ይመ
ጣላችኋል ። ምዕ ፪ ፡ ፴፰ ። ኢሳ ፴፭ ፡ ፲ ።
አስቀድሞ የመረጠው ኢየሱስ ክርስቶስን ይሰድላ ፳
ችኋል ። ዳን ፯ ፡ ፳፪ - ፳፯ ። ሮሜ ፰ ፡ ፳፩ ። ራእ ፳ ፡ ፯ ።
ሁሉን እስኪያከናውን ድረስ አስቀድሞ በነበሩ በቅ ፳፩
ዱሳን ነቢያቶቹ አንደበት እግዚአብሔር እንደ ተና
ገረ ሰማይና ምድር እሱን ተስፋ የሚያደርጉት ።
ሙሴም አባቶቻችን እንዲህ ብሏቸዋል እግዚአብ ፳፪
ሔር አምላካችን ከወንድሞቻችሁ እንደኔ ነቢይ ያስ
ነሣላችኋል የሚያስተምራችሁን ሁሉ እሱን ስሙት ።
ዘዳግ ፲፰ ፡ ፲፭ - ፲፰ ።
ያንን ነቢይ የማትሰማው ወገን ሁሉ ከወገኖቹ ፳፫
ትለይ ። ምዕ ፲፫ ፡ ፴፰ - ፵፩ ። ዕብ ፪ ፡ ፪ - ፫ ።
ከነቢዩ ከሳሙኤል ጀምሮ ከነሱና በኋላ የተነሡ ነቢ ፳፬
ያት ሁሉ ስለ እነዚህ ቀኖች ተናግረዋል አስተምረ
ዋል ።
እናንተም የነቢያት ልጆች እግዚአብሔር ለአባቶ ፳፭
ቻችን በሠራው ሥርዓት የተወለዳችሁ ናችሁ አብ

ብርሃም በዘርእከ ይትባረኩ ኵሎሙ አሕዛበ ምድር ።
፳፮ ወለክሙ አቅደመ አንሥኦቶ እግዚአብሔር ለወልዱ ወፈነዎ ይባርክሙ ከመ ትንስሑ ኵልክሙ እምእከይክሙ ።

ምዕራፍ ፬ ፤

ክፍል ፲ወ፮ ፡ በእንተ ሊቃነ ክህናት ወመገብተ ምኵራብ ።

፩ ወእንዘ ይነግሮሙ ለሕዝብ መጽኡ ሊቃነ ክህናት ወመገብተ ምኵራብ ወሰዱቃውያን ።

፪ ወቀንኡ ላዕሌሆሙ እስመ ይሜህርዎሙ ለሕዝብ ወይነግርዎሙ በእንተ ኢየሱስ ከመ ሐይወ እሙታን ።

፫ ወአኀዝዎሙ ወአውዐልዎሙ ሙዓለ እስከ ጌሠም እስመ ወድአ መስየ ።

፬ ወብዙኃን ሰብእ እለ ሰምዕዎ ለዝ ነገር ወአምኑ ወኮኑ ኍልቆሙ ለእደው እለ አምኑ መጠነ ኀምሳ ምእት ።

፭ ወእምዝ በሳኒታ ተጋብኡ መላእክት ወረበናት ወጸሐፍት በኢየሩሳሌም ።

፮ ወሐና ሊቀ ክህናት ወቀያፋ ወዮሐንስ ወእለ እስክንድሮስ ወኵሎሙ ዘመደ ክህናት ።

፯ ወአቀምዎሙ ማእከለ ዐውድ ወሐተትዎሙ ወይቤልዎሙ በኃይለ መኑ ወበስመ መኑ ገበርክሙ ዘንተ አንትሙ ።

ክፍል ፲ወ፯ ፡ በእንተ አውሥኦተ ጴጥሮስ ።

፰ ወመልአ መንፈስ ቅዱስ ሶቤሃ ላዕለ ጴጥሮስ ወይቤሎሙ ስምዑ መላእክተ ሕዝብ ወረበናት ።

፱ ለእመሁ ንሕነ ንትኴነን ኀቤክሙ በእንተ ረድኤተ ሕሙም ዘኮነ ዮም በምንትኑ እንከ ሐይወ ዝንቱ ።

፲ አእምሩ እንከ ጥዩቀ ኵልክሙ ወኵሉ ቤተ እስራኤል ከመ በስሙ ለኢየሱስ ክርስቶስ ናዝራዊ ዘአንትሙ ቀተልክምዎ ወእግዚአብሔር አንሥኦ እሙታን ወበቱ ሐይወ ዝንቱ ወቆመ ቅድሜክሙ ።

፲፩ እስመ ውእቱ እብን ዘመነንክምዎ አንትሙ ነደቅት ወውእቱ ኮነ ውስተ ርእሰ ማዕዘንት ።

፲፪ ወአልቦ ካልእ ሕይወት በዘየሐይዉ ወአልቦ ካልእ ስም በታሕተ ሰማይ ዘይትወሀብ ለእጓለ እመሕያው ።

ርሃምን በዘርህ የምድር አሕዛብ ሁሉ ይባረካሉ ብሎ ታልና ። ዘፍ ፲፪ ፡ ፫ ። ፳፪ ፡ ፲፰ ። ሮሜ ፱ ፡ ፬-፰ ።
እግዚአብሔር አስቀድሞ ለእናንተ ልጁን አስነሣላ ፳፮
ችሁ ፡ ሁላችሁ ከክፋታችሁ እንድትመለሱ ሊባርካ
ችሁ ላከላችሁ ። ምዕ ፲፫ ፡ ፵፮ ።

ምዕራፍ ፬ ፤

ክፍል ፲፮ ፡ ስለ ካህናት አለቆችና ፡ ስለ ምኵራብ ሹማምት ።

ሕዝቡንም ሲያስተምራቸው የካህናት አለቆች የምኵራቡ ሹማምትና ሰዱቃውያን መጡ ። ነህ ፪ ፡ ፲ ። ሉቃ ፳፪ ፡ ፬-፶፪ ። ፩

ከሙታን እንደተነሣም የኢየሱስን ነገር ለሕዝቡ ይነግሯቸው ያስተምሯቸው ነበርና ቀኑባቸው ። ፪

ይዘውም ቀኑን ሁሉ አዋሏቸው ፣ በማግሥቱም ቀጠሯቸው ፈጽሞ መሽቶ ነበርና ። ፫

ይህንንም ነገር ሰምተው ያመኑ ብዙ ሰዎች ናቸው የመኑት ሰዎች ቍጥርም አምስት ሺሕ ያህል ሆነ ። ምዕ ፪ ፡ ፵፯ ። ፬

ከዚህም በኋላ በማግሥቱ አለቆች መምህራን ጻፎች በኢየሩሳሌም ተሰበሰቡ ። ፭

የካህናቱ አለቃ ሐና ቀያፋ ዮሐንስና እለእስክንድሮስ የካህናት ወገን ሁሉ ተሰበሰቡ ። ሉቃ ፫ ፡ ፪ ። ዮሐ ፲፩ ፡ ፵፱ ። ፮

በአደባባይም አቆሙና እናንተ ይህንን በማን ስም በማንስ ኃይል አደረጋችሁት ? ብለው መረመሯቸው ። ዘፀ ፪ ፡ ፲፬ ። ማቴ ፳፩ ፡ ፳፫ ። ምዕ ፯ ፡ ፳፯ ። ፯

ክፍል ፲፯ ፡ ጴጥሮስ ስለ ሰጠው መልስ ።

ያን ጊዜም በጴጥሮስ መንፈስ ቅዱስ መላበትና እንዲህ አላቸው ፡ የሕዝብ አለቆችና መምህራን ሆይ ! ስሙ ። ሉቃ ፲፪ ፡ ፲፩ ። ፰

ዛሬ ለበሽተኛው በተደረገው ረድኤት ምክንያት በእናንተ ዘንድ እኛ የሚፈረድብን ከሆነ እንግዲያ ይህ ሰው በምን ዳነ ? ዮሐ ፲ ፴፪ ። ፱

እንግዲህ እናንተ ሁላችሁ የእስራኤል ወገን ሁሉ እናንተ በገደላችሁት እግዚአብሔር ከሙታን ለይቶ በአስነሣው በናዝሬቱ በኢየሱስ ክርስቶስ ስም ይህ ሰው እንደዳነና በፊታችሁ እንደቆመ በጉላ በተረዳ እወቁ ። ምዕ ፫ ፡ ፲፮ ። ፲

እርሱ እናንተ አናጢዎች የናቃችሁት ደንጊያ ነውና ያም የመዓዝን ራስ ሆኗልና ። ኢሳ ፡ ፳፰ ፲፯ ፡ መዝ ፻፲፰ ፳፪ ፡ ማቴ ፳፩ ፵፪ ። ፲፩

ሰዎች የሚድኑበት ሌላ ሕይወት የለም ፡ ከሰማይ በታችም ለሰው ልጅ የሚሰጥ ሌላ ስም የለምና ። ፲፪

## ክፍል ፲ወ፯ ፡ በእንተ ከሊአ ትምህርት ።

፲፫ ወሰበ ርእይዎሙ ለጴጥሮስ ወለዮሐንስ ከመ ገሀደ
ይነግርዎሙ አእመርዎሙ ከመ ሰብእ የውሃን እሙ
ንቱ ወኢየአምሩ መጽሐፈ ወአንከርዎሙ እስመ
የአምርዎሙ ዘልፈ ከመ ምስለ ኢየሱስ ሀለዉ ።
፲፬ ወይሬእይዎ ለዝኩሂ ብእሲ ዘሐይወ ይቀውም ምስ
ሌሆሙ ወኃጥኡ ዘይብሉ ወዘይነብቡ ።
፲፭ ወአእተትዎሙ ሐቀ እምዐውድ ወተናገሩ በበይናቲ
ሆሙ ።
፲፮ ወይቤሉ ምንተ ንሬስዮሙ ለእሉ ሰብእ ናሁ ተዐ
ውቀ ትምህርቶሙ በኀበ ኵሎሙ እለ ይነብሩ ኢየ
ሩሳሌም ወገሃደ ኮነ ወኢንክል ክቢቶቶ ።
፲፯ ዳእሙ ከመ ፈድፋደ ኢይብዛኅ በላዕለ ሕዝብ ንገ
ሥዮሙ ከመ ዳግመ ኢይንግሩ በስሙ ለኢየሱስ
ለሰብእ ።
፲፰ ወጸውዕዎሙ ወይቤልዎሙ ግሙራ ኢትንግሩ ወኢ
ትምሀሩ በስሙ ለኢየሱስ ።

## ክፍል ፲ወ፰ ፡ በእንተ አውሥኦተ ሐዋርያት ።

፲፱ ወተሰጥውዎሙ ጴጥሮስ ወዮሐንስ ወይቤልዎሙ
ይረትዕኑ በቅድመ እግዚአብሔር ኪያክሙ ንስማዕ
ወአኮ ለእግዚአብሔር ፤ ፍትሑ እስኩ ለሊክሙ ።

፳ ንሕነሰኬ ኢንክል ከቢቶቶ ለዝንቱ ነገር ።

፳፩ ወእምዝ ገሠፅዎሙ ወኀደግዎሙ ሰበ ኃጥኡ በዘይ
ኴንንዎሙ እስመ ኵሉ ሕዝብ የአኵቱ እግዚአብ
ሔርሃ በእንተ ውእቱ ተአምር ዘኮነ ።
፳፪ እስመ ፈድፋደ እምአርበዓ ዓመት ለውእቱ ብእሲ
ዘበላዕሌሁ ኮነ ዝ ተአምረ ሕይወት ።
፳፫ ወተፈቲሖሙ ሖሩ ኀበ ሰብአሙ ወነገርዎሙ ኵሎ
ዘይቤልዎሙ ሊቃነ ካህናት ወረበናት ።

## ክፍል ፲ወ፱ ፡ በእንተ አእኵቶቶሙ እግዚአብሔርሃ ።

፳፬ ወሰሚዖሙ ዘንተ አንሥኡ ቃሎሙ ኅቡረ ኀበ እግዚ
አብሔር ወይቤሉ አንተ እግዚአብሔር አምላክ ዘገ
በርከ ሰማየ ወምድረ ወባሕረ ወኵሎ ዘውስቴቶሙ ።

፳፭ ዘለሊከ ነበብከ በመንፈስ ቅዱስ በአፈ ዳዊት ገብርከ
አቡነ ፤ ወትቤ ለምንት አንገለጉ አሕዛብ ወሕዝብኒ
ነበቡ ከንቶ ።
፳፮ ወተንሥኡ ነገሥተ ምድር ፤ ወመላእክትኒ ተጋብኡ
ምስሌሆሙ ኅቡረ ፡ ላዕለ እግዚአብሔር ወላዕለ
መሲሑ ።
፳፯ አማን አንገለጉ በዛቲ ሀገር ላዕለ ቅዱስ ወልድከ



## ክፍል ፲፯ ፡ ትምህርትን ስለ መከልከል ።

ጴጥሮስና ዮሐንስም ግልጥ አድርገው ሲናገሩ በዩ ፲፫
ዋቸው ጊዜ ያልተማሩና መጽሐፍ የማያውቁ ሰዎች
እንደሆኑ አወቋቸው ፤ ግን አደነቋቸው ሁል ጊዜም
ከኢየሱስ ጋር እንደነበሩ ያውቋቸው ነበርና ።
ያንን የዳነው ሰው ከነርሱ ጋራ ቁሞ ያዩት ነበርና ፲፬
የሚናገሩት የሚመልሱት አጡ ። ምዕ ፫ ፱ ።
ከአደባበይም ጥቂት ፈቀቅ አደረጓቸውና እርስ ፲፭
በርሳቸው እንዲህ ብለው ተነጋገሩ ።
እነዚህ ሰዎች ምን እናድርጋቸው እነሆ ትምህር ፲፮
ታቸው በኢየሩሳሌም በሚኖሩት ሁሉ ታወቀ ግልጥ
ሆነ ልንደብቀው አንችልም ። ዮሐ ፲፩ ፵፯ ።
ግን በሕዝቡ ላይ እጅግ እንዳይስፋፋ ዳግመኛ በኢ ፲፯
የሱስ ስም ሰውን እንዳያስተምሩ እንገሥፃቸው ።

ጠርተውም በኢየሱስ ስም ፈጽሞ እንዳታስተምሩ ፲፰
አሏቸው ።

## ክፍል ፲፰ ፡ ሐዋርያት ስለ ሰጡት መልስ ።

ጴጥሮስና ዮሐንስም እንዲህ ብለው መለሱላቸው ፤ ፲፱
በእግዚአብሔር ፊት እግዚአብሔርን ያይደለ እና
ንተን ልንሰማ ይገባልን ? እስኪ እናንተ ራሳችሁ
ፍረዱ ። ምዕ ፭ ፳፱ ። ገላ ፩ ፲ ።
እኛስ ይህን ነገር ልንሸሽገው አንችልም ። ምዕ ፩ ፰ ፳
ምዕ ፳፪ ፲፭ ፡ ፩ ዮሐ ፩ ፩ ።
የሚፈርዱበት ምክንያት ባጡ ጊዜም ገርፈው ለቀ ፳፩
ቋቸው ስለ ተደረገው ተአምራት ሕዝቡ ሁሉ እግዚ
አብሔርን ያመሰግኑ ነበርና ።
ይህ የድኅነት ተአምር የተፈጸመበት ለዚያ ሰው ፳፪
ከአርባ ዘመን በልጦት ስለ ነበረ ።
ተፈትተውም ወደ ሰዎቻቸው ሄዱና ፤ የካህናት አለቆ ፳፫
ችና ሽማግሌዎችም ያሏቸውን ሁሉ ነገሯቸው ።

## ክፍል ፲፱ ፡ እግዚአብሔርን ስለ ማመስገናቸው ።

ይህንንም በሰሙ ጊዜ በአንድነት ቃላቸውን ወደ እግ ፳፬
ዚአብሔር ከፍ ከፍ አድርገው እንዲህ አሉ ፤ ሰማ
ይን ምድርንና ባሕርን በውስጣቸው ያለውን የፈጠ
ርክ አንተ እግዚአብሔር ! ። መዝ ፻፵፭ ፲፮ - ፲፯ ።
መዝ ፻፫ ፩ ። ኤር ፳ ፲፫ ።
አንተ ራስህ በአባታችን በዳዊት አድረህ በመን ፳፭
ፈስ ቅዱስ የተናገርክ እንዲህ ብለህ "አሕዛብ ለምን
ተሰበሰቡ ፡ ሕዝቡስ ለምን ከንቱ ነገር ተናገሩ ።
መዝ ፪ ፩ - ፫ ።
የምድር ነገሥታትስ ለምን ተነሡ ፤ አለቆችስ በእግዚ ፳፮
አብሔርና በክርስቶስ ላይ አብረው ለምን ዶለቱ ?" ።
ጴንጤናዊው ጲላጦስና ሄሮድስ ከወገኖቻቸው የእስ ፳፯

፫፻፳፬ ግብረ ሐዋርያት ፬ ።

ኢየሱስ ዘቀባእከሁ ፡ ሄሮድስ ወጲላጦስ ጴንጤናዊ ምስለ ሕዘቢሆሙ ወሕዝበ እስራኤል ።
፳፰ ከመ ይግበሩ በከመ ሥርዓት እዴከ ወምክርከ ከመ ይኩን ።
፳፱ ወይዜኒ እግዚኦ ርኢ ትምክሕቶሙ ወሀበሙ ለአግብርቲከ ገሀደ ይንግሩ ቃለከ ።

፴ ትስፋሕ እዴከ ወትገብር ትእምርተ ወመንክረ በስመ ወልድከ ኢየሱስ ክርስቶስ ንጹሕ ።

፴፩ ወእንዘ ይጼልዩ አድለቅለቀ ውእቱ መካን ኀበ ሀለዉ ይነብሩ ኅቡረ ጉቡአን ወመልአ መንፈስ ቅዱስ ዲበ ኵሎሙ ወነገሩ ቃለ እግዚአብሔር ገሃደ ።

ክፍል ፰ ፡ በእንተ ማኅበር ።

፴፪ ወኵሎሙ እለ አምኑ በአሐዱ ልብ ወበአሐቲ ነፍስ ወአልበ እምውስቴቶሙ ዘይብል ዝስ ዚአየ ንዋይ ፡ አላ ዘኵሎሙ ኅቡረ ።

፴፫ ወዓቢየ ኃይለ ይገብሩ ሐዋርያት ስምዓ ተንሥአቱ ለእግዚእ ኢየሱስ ወዐቢይ ሞገስ በሙ በኀበ ኵሉ ።

፴፬ ወአልቦ እምውስቴቶሙ ጽኑስ ፡ ወኵሉ ዘበ ቤት ወዓፀደ ይሠይጡ ወያመጽኡ ።
፴፭ ወያነብሩ ታሕተ እገሪሆሙ ለሐዋርያት ወእሙንቱ ይከፍሉ ለጽኑሳን ወለለ አሐዱ በከመ መፍቅዱ ።

፴፮ ወሀሎ አሐዱ ብእሲ ዘስሙ ዮሴፍ ዘይብልዎ በርናባስ እምውስተ ሐዋርያት ወበትርጓሜሁ ይብልዎ ወልደ ፍሥሐ ሌዋዊ ዘምድረ ቆጵሮስ ።

፴፯ ወበ ገራህት ወሤጠ ወአምጽአ ሤጦ ወአንበረ ታሕተ እግረ ሐዋርያት ።

ምዕራፍ ፭ ፤
ክፍል ፰ወ፩ ፡ በእንተ ሐናንያ ወብእሲቱ ።

፩ ወሀሎ ፩ዱ ብእሲ ዘስሙ ሐናንያ ወስመ ብእሲቱ ሰጲራ ወሤጡ ዐፀዶሙ ።
፪ ወቀሰጡ መንፈቀ ሤጡ ተማኪሮሙ ምስለ ብእሲቱ ወአምጽኡ መንፈቀ ሤጡ ወአንበሩ ታሕተ እግረ ሐዋርያት ።

፫ ወይቤሎ ጴጥሮስ ኦ ሐናንያ እፎ መልአ ሰይጣን ውስተ ልብከ ከመ ተሐስዎ ለመንፈስ ቅዱስ ወትቀስጥ እምሤጠ ዐፀድከ ።

የሐዋርያት ሥራ ፬ ።

ራሔልን ሕዝብ ጭምር በመረጥከው በልጅህ በኢየሱስ ላይ በዚች አገር በውነት ዶለቱ ። ኢሳ ፷፩ ፩፡
እጅህ እንደሠራቸው እንደ ምክርህ ይሆን ዘንድ ሊያደርጉ ። ምዕ ፪ ፳፫ ። ፳፰
አሁንም አቤቱ ! ትዕቢታቸውን አይተህ ቃልህን በግልጥ ያስተምሩ ዘንድ ለባሮችህ ፍቀድላቸው ። ፳፱
ኢሳ ፶፰ ፩፡ ሕዝ ፪ ፯፡ ምዕ ፲፱ ፰ ።
ሥልጣንህን ትገልጥ ዘንድ በንጹሕ ባሕርይ ልጅህ በኢየሱስ ክርስቶስ ስም ተአምራትና ድንቅ ሥራ ትሠራ ዘንድ ። ምዕ ፫ ፮-፲፯ ። ፴
ሲጸልዩም በአንድነት ተሰብስበው የነበሩበት ቦታ ተናወፀ በሁሉም ላይ መንፈስ ቅዱስ አደረባቸውና የእግዚአብሔርን ቃል ያለ ፍርሃት አስተማሩ ። ፴፩

ክፍል ፰፡ ስለ አንድነት ።

ያመኑት ሁሉ አንድ ልብ አንድ አፍ ሆነው ይኖሩ ነበር ፡ ከመካከላቸውም ይህ የኔ ገንዘብ ነው የሚል አልነበረም ፡ የሁሉም ገንዘብ በአንድነት ነበር እንጂ ምዕ ፪ ፵፬ ። ሮሚ ፲፭ ፭፡ ፩ ጴጥ ፫ ፰ ። ፴፪
ሐዋርያትም ጌታችን ኢየሱስ ለመነሣቱ ምስክር ሊሆን ታላላቅ ሥራ ይሠሩ ነበር ፡ በሕዝቡም ዘንድ ፍጹም መወደድ ነበራቸው ። ምዕ ፪ ፵፯ ። ፴፫
ከእነሱ መካከል ችግረኛ አልነበረም ፡ ቤትና ቦታ ያለው ሁሉ እየሸጡ ገንዘቡን ያመጡ ነበር ። ምዕ ፪ ፵፭ ። ፴፬
አምጥተውም ከሐዋርያት እግር በታች ያኖሩት ነበር ፡ እነርሱም ለችግረኞች ለያንዳንዱ እንደ ችግሩ ያከፍሉት ነበር ። ዘዳግ ፲፭ ፡ ፲፩ ። ኢሳ ፶፫ ፡ ፯ ። ፴፭
ከሐዋርያትም መካከል ዮሴፍ የሚባል በርናባስ ብለው የሚጠሩት አንድ ሰው ነበር ፡ ትርጓሜውም የደስታ ልጅ ማለት ነው ፡ ከቆጵሮስ አገር የመጣ የሌዋ ወገን ። ፴፮
እርሻ ነበረውና ሸጦ ዋጋውን አምጥቶ ከሐዋርያት እግር በታች አኖረው ። ፴፯

ምዕራፍ ፭ ፤
ክፍል ፰፩ ፡ ስለ ሐናንያና ስለ ሚስቱ ።

ሐናንያ የሚባል አንድ ሰው ነበረ ፡ ሚስቱም ሰጲራ ትባል ነበር ፡ በታቸውን ሸጡ ። ፩
ከሚስቱም ጋራ ተማክረው የዋጋውን እኩሌታ ከፍለው አስቀሩ ፡ የዋጋውንም እኩሌታ አምጥተው ከሐዋርያት እግር በታች አስቀመጡ ። ምዕ ፬ ፡ ፴፯ ። ኢያ ፡ ፯ ፡ ፩ ። ፩ ጢሞ ፯ ፡ ፲ ። ፪
ጴጥሮስም ሐናንያ ሆይ ! መንፈስ ቅዱስን ዋሽ አድርገኸው የቦታህን ዋጋ ከፍለህ ትደብቅ ዘንድ ሰይጣን በልብህ እንዴት አደረ ! ? ። ዘኍ ፴ ፡ ፪ ። ዘዳግ ፳፫ ፡ ፳፩ ። መክ ፭ ፡ ፬ ። ዮሐ ፲፫ ፡ ፪ ። ፫

፬ አኮኑ ለከ ነበረ እምቅድመ ትሢጦ ወሰበኒ ሤጥከ
በፈቃድከ ለምንትኬ ሐለይከ በልብከ ትግበር ከመዝ
ለእግዚአብሔርኬ ሐሰውከ ወአኮ ለሰብእ ።
፭ ወሰሚዖ ዘንተ ነገረ ሐናንያ ተነጽሐ ወሞተ ፡ ወኮነ
ዐቢይ ግርማ ወፈርሁ ኵሎሙ እለ ሰምዑ ።
፮ ወተንሥኡ መሐዛት አምኔሆሙ ወፆርዎ ወገነዝዎ
ወአውጽእዎ ወቀበርዎ ።
፯ ወእምዝ እምድኅረ ሠለስቱ ሰዓት መጽአት ብእሲቱ
ወኢያእመረት ።
፰ ወይቤላ ጴጥሮስ ንግርኒ እስኩ በመጠነ ዝኑ ሤጥ
ክሙ ዐፀደክሙ ፡ ወትቤ እወ ከማሁ ።
፱ ወይቤላ ጴጥሮስ በእፎ አንከ ኅበርክሙ ታመክርዎ
ለመንፈስ ቅዱስ ናሁኬ እገሪሆሙ ለእለ ቀበርዎ
ለምትኪ ኀበ ኆኅት ወእሙንቱ ይወስዱኪ ኪያኪኒ ።
፲ ወተነጽሐት ሶቤሃ ታሕተ እገሪሁ ወሞተት ፡ ወቦኡ
ወራዙት ወረከብዋ በድና ወወሰድዋ ወቀበርዋ
ኀበ ምታ ።
፲፩ ወኮነ ዓቢይ ግርማ ወፈርሁ ኵሎሙ አብያተ ክርስ
ቲያናት ወእለ ሰምዕዎ ለዝ ነገር ።
፲፪ ወበእደዊሆሙ ለሐዋርያት ይትገበር ተአምር ወመ
ንክር ብዙኅ በውስተ ሕዝብ ፡ ወሀለዉ ኅቡረ በቤተ
መቅደስ ውስተ ሕዋረ ሰሎሞን ።
፲፫ ወእምዝ አንከ አልቦ ዘተኀበለ ይስሐቦሙ ዳእሙ
አከበርዎሙ ሕዝብ ወአዕበይዎሙ ።
፲፬ ወብዙኃን ይትዌሰኩ እለ አምኑ በእግዚእነ ወብዙ
ኃን እደው ወአንስት ።

ክፍል ፳ወ፪ ፡ በእንተ ፈውሶቶሙ ድውያን ።

፲፭ ወያመጽኡ ድውያነ በዐራታት ወያነብርዎሙ ከመ
ይብጽሖሙ ጽላሎቱ ለጴጥሮስ ሶበ የኀልፍ ወይት
ፌወሱ እምደዌሆሙ ።
፲፮ ወይመጽኡ ብዙኃን እምአህጉረ አድያም ዘኢየሩሳ
ሌም ወያመጽኡ ድውያነ ወእለ አጋንንት አኩያን
ወየሐይዉ ኵሎሙ ።

ክፍል ፳ወ፫ ፡ በእንተ ቅንአት ዘሊቃነ ካህናት ።

፲፯ ወተንሥኡ ሊቃነ ካህናት ወእለ ምስሌሆሙ ወሕ
ዝብ ሰዱቃውያን ወቀንኡ ዲቤሆሙ ።
፲፰ ወአኃዝዎሙ ለሐዋርያት ወአውዓልዎሙ ሙዓለ
ውስተ ቤተ ሞቅሕ ።
፲፱ ወመልአከ እግዚአብሔር አርኃወ አናቅጸ ቤተ
ሞቅሕ በሌሊት ወአውፅኦሙ ወይቤሎሙ ።
፳ ሑሩ ባኡ ምኵራበ ወመሀርዎሙ ለሕዝብ ዘንተ
ነገረ ሕይወት ።



ሳትሸጠው ያንተ አልነበረምን ? ስትሸጠውም በፈ ፬
ቃድህ ነው ፡ እንዲህ ልታደርግ በልብህ ለምን አሰ
ብክ፡ ሰውን ያይደለ እግዚአብሔርን እኮ አታለልከው።
ሐናንያም ይህን በሰማ ጊዜ ፍግም ብሎ ወድቆ ሞተ ፭
ስኑ ፍርሃት ሆነ ፡ የሰሙትም ሁሉ ፈሩ ።
ከእነሱም ጐልማሶች ተነሥተው ተሸክመው ወስደው ፮
ገንዘው ቀበሩት ። ዘሌ ፲ ፡ ፬ - ፭ ።
ይህም በሆነ ከሦስት ሰዓት በኋላ ሚስቱ መጣች ፡ ፯
በዓ. የሆነውን አላወቀችምና ወደቤት ገባች ።
ጴጥሮስም እስኪ ንገሪኝ በታችሁን የሸጣችሁት ለዚ ፰
ህ ያህል ነውን ? አላት ፡ እሷም አዎን እንዲሁ ነው
አለች ።
ጴጥሮስም እንግዲህ መንፈስ ቅዱስን ትፈታተኑት ፱
ዘንድ እንዴት ተባበራችሁ ? እነሆ ባልሽን የቀበሩት
ሰዎች ከበር ደርሰዋል አንቺንም ይወስዱሻል አላት።
ዘዳግ ፮ ፡ ፲፮ ። መዝ ፺፭ ፡ ፱ ። ማቴ ፬ ፡ ፲፪ ።
ያን ጊዜም ከእግሩ በታች ወድቃ ሞተች ፡ ጐልማ ፲
ሶችም በገቡ ጊዜ በድን ሁና አገኙዋትና ወስደው
ከባሏ ዘንድ ቀበሯት ።
ታላቅ ፍርሃት ሆነ ፡ አብያተ ክርስቲያናትና ይህን ፲፩
ነገር የሰሙት ሁሉ ፈሩ ።
በሐዋርያት እጅ ፡ በሕዝቡ ዘንድ ተአምራትና ድንቅ ፲፪
ድንቅ ሥራ ይሠሩ ነበር ፡ በቤተ መቅደስም በሰሎ
ሞን ወለል በአንድነት ይጸልዩ ነበር ። ምዕ ፫ ፡ ፲፩ ።
ከዚህ በኋላ ሊጣላቸው የደፈረ የለም ፡ ሕዝቡ አክበ ፲፫
ሯቸው ክፍ ክፍ አደረጓቸው እንጂ ። ምዕ ፪ ፡ ፵፯ ።
ብዙዎቹም በጌታችን እያመኑ ይጨመሩ ነበር ፡ ወን ፲፬
ዶችም ሴቶችም ብዙዎች ነበሩ ። ምዕ ፪ ፡ ፵፯ ።

ክፍል ፳፪ ፡ ድውያንን ስለ መፈወሳቸው ።

ድውዮችንም በአልጋ እያመጡ ጴጥሮስ አልፎ ፲፭
ሲሄድ ጥላው ያርፍባቸው ዘንድ በመንገድ ያስቀም
ጧቸው ከደዌያቸውም ይፈወሱ ነበር ። ማቴ ፱ ፡ ፳፩።
ከኢየሩሳሌም አውራጃ ሀገሮች ብዙዎች ይመጡ ፲፮
ነበር ፡ የታመሙት ክፉዎች አጋንንት የያዟቸውን
ያመጡ ነበር ሁሉም ይድኑ ነበር ። ማር ፲፮ ፡ ፲፯ ።

ክፍል ፳፫ ፡ ስለ ካህናቱ አለቆች ቅናት ።

የካህናት አለቆችና አብረዋቸው የነበሩት የሰዱቃው ፲፯
ያን ወገኖች ቀንተው በእነርሱ ላይ ተነሡ ።
ሐዋርያትንም ይዘው በግዞት ቤት አንድ ቀን ሞያ ፲፰
አዋሏቸው ። ሉቃ ፳፩ ፡ ፲፪ ።
የእግዚአብሔር መልአክ በሌሊት የግዞቱን ቤት ከፍቶ ፲፱
አወጣቸውና እንዲህ አላቸው ። መዝ ፴፬ ፡ ፮ ። ኢሳ
፷፩ ፡ ፩ ። ምዕ ፲፪ ፡ ፯ ።
ሂዱ ወደ ምኵራቡ ግቡና ለሕዝቡ ይህንን የሕይ ፳
ወት ትምህርት አስተምሩአቸው ። ኤር ፮ ፪ ።

| | ግብረ ሐዋርያት ፭ ። | የሐዋርያት ሥራ ፭ ። | |
|---|---|---|---|
| ፳፩ | ወሰሚዖሙ ዘንተ ጌሡ ነግሀ በጽባሕ ወቦኡ ምኵራበ ወመሀሩ ወሊቃነ ካህናትሰ ወእለ ምስሌሆሙ አስተጋብኡ ዐውዶሙ ወኵሎ ሊቃነ ቤተ እሥራኤል ወለአኩ ቤተ ሞቅሕ ያምጽእዎሙ ለሐዋርያት ። | ይህንንም በሰሙ ጊዜ ጧት ገሥግሦው ወደ ምኵራብ ገቡና አስተማሩ ፡ የካህናቱ አለቆችና አብረዋቸው የነበሩት ግን ጉባኤያቸውን የእስራኤልን ቤት አለቆችም ሁሉ ሰበሰቡ ፡ ሐዋርያትንም ያመጡአቸው ዘንድ ወደ እሥር ቤቱ ላኩ ። ምዕ ፬ ፡ ፭ - ፯ ። | ፳፩ |
| ፳፪ | ወበጽሐ ወዐልያኒሆሙ ወኃጥእዎሙ ወተሠውጡ ወነገርዎሙ ። | ሎሌዎቻቸውም መጥተው አጧቸውና ተመልሰው ነገሯቸው ። | ፳፪ |
| ፳፫ | ወይቤልዎሙ ረከብነ ቤተ ሞቅሕ ንሡገ ወቅቱረ ወዝጉሐ እንተ ኵለሄ ወሠገራተ የዐቅቡ አናቅጺሁ ወአርኃውነ አልቦ ዘረከብነ በውስጥ ። | እሥር ቤቱን ተቈልፎ ተጠርቆ ዙሪያውን ተዘግቶ አገኘነው ፡ ወታደሮቹም በሩን ይጠብቁ ነበር ፡ ግን ከፍተን በገባን ጊዜ ከውስጥ ያገኘነው የለም አሏቸው ። | ፳፫ |
| ፳፬ | ወሰሚዖሙ ዘንተ ነገረ ሊቃነ ካህናት ወመገብተ ምኵራብ ኃጥኡ ዘይገብሩ ወይቤሉ ምንትኑ እንጋዝ ነገር ። | የካህናት አለቆችና የምኵራብ ሹማምንትም የሚያደርጉትን አጥተው እንጃ ይህ ነገር ምን ይሆን ? አሉ ። | ፳፬ |
| ፳፭ | ወመጽአ አሐዱ ወይቤሎሙ ነዮሙ እሙንቱ እደው እለ ሞቃሕክምዎሙ ውስተ ምኵራብ ይቀውሙ ወይሜህሩ ለሕዝብ ። | አንድ ሰው መጥቶ ያሠራችኋቸው እነዚያ ሰዎች እነሆ በምኵራቡ ውስጥ ናቸው ፡ ቆመውም ሕዝቡን ያስተምራሉ አሏቸው ። | ፳፭ |
| ፳፮ | ወእምዝ ሖረ መጋቤ ምኵራብ ምስለ ወዓልያኒሁ ያምጽእዎሙ እንዘ ይየውህዎሙ እስመ ይፈርህዎሙ ለሕዝብ ኢይውግርዎሙ ። | ከዚህም በኋላ አታለው ሊያመጡአቸው የምኵራቡ ሹም ከሎሌቹ ጋር ሂዶ በደንጊያ እንዳይወግሯቸው ሕዝቡን ይፈሩ ነበርና ። ማቴ ፲፬ ፡ ፭ ። | ፳፮ |
| ፳፯ | ወአምጽእዎሙ ወአቀምዎሙ ማእከለ ዓውድ ወሐተትዎሙ ሊቃነ ካህናት ። | አምጥተውም በአደባባይ መካከል አቆሟቸው የካህናት አለቆችም መረመሯቸው ። | ፳፯ |
| ፳፰ | ወይቤልዎሙ አኮኑ ከላእናክሙ ከመ ኢትምሀሩ በስሙ ለኢየሱስ ወኢለመኑሂ ወናሁ መላእክምዋ ትምህርተክሙ ለኢየሩሳሌም ወትፈቅዱኑ ታግብኡ ላዕሌነ ደሞ ለዝ ብእሲ ። | በኢየሱስ ስም እንዳታስተምሩ ከልክናችሁ አልነበረም ? እነሆ ኢየሩሳሌምን ትምህርታችሁን መላችኋት ፡ የዚያን ሰው ደም በእኛ ልትመልሱ ትሻላችሁን ? አሏቸው ። ምዕ ፬ ፡ ፲፰ ። ማቴ ፳፯ ፡ ፳፭ ። | ፳፰ |
| ፳፱ | ወተሰጥዎሙ ጴጥሮስ ምስለ ሐዋርያት ወይቤሎሙ ይኄይሰነ ናድሉ ለእግዚአብሔር እምነ አድልዎ ለሰብእ ። | ጴጥሮስም ከሐዋርያት ጋር መልሶ እንዲህ አላቸው ፡ ለሰው ከማድላት ይልቅ ለእግዚአብሔር ማድላት ይበልጣል ። ፬ ፡ ፲፱ ። | ፳፱ |
| ፴ | አምላከ አበዊነ አንሥኦ ለኢየሱስ ዘአንትሙ ዐለውክምዎ ወሰቀልክምዎ ዲበ ዕፅ ወቀተልክምዎ ። | የአባቶቻችን አምላክ እናንተ ከዳችሁ በዕንጨት ላይ ሰቀላችሁ የገደላችሁት ኢየሱስን አስነሣው ። | ፴ |
| ፴፩ | ኪያሁ ረሰዮ እግዚአብሔር መልአከ ሕይወት ወአልዐሎ በየማኑ ወወሀበሙ ለእስራኤል ንስሐ ከመ ይትኃደግ ሎሙ ኃጢአቶሙ ። | እግዚአብሔር እሱን የሕይወት ባለ ቤት አደረገው በቀኙም አስቀመጠው ፡ እስራኤልም ኃጢአታቸው እንዲሠረይላቸው ንስሐን ሰጣቸው ። ምዕ ፪ ፡ ፴፫ ። | ፴፩ |
| ፴፪ | ወንሕነሰ ሰማዕቱ ለዝንቱ ነገር ወመንፈስ ቅዱስ ዘወሀበሙ እግዚአብሔር ለእለ የአምኑ በቱ ። | እኛ ስለዚህ ነገር ምስክሮቹ ነን እግዚአብሔር ለሚያምኑበት የሰጣቸው መንፈስ ቅዱስም ምስክር ነው ። ሉቃ ፳፬ ፡ ፵፰ ። ዮሐ ፲፭ ፡ ፳፮ - ፳፯ ። | ፴፪ |
| ፴፫ | ወሰሚዖሙ ዘንተ ተምዕዑ ወሐቀዩ ስነኒሆሙ ወፈቀዱ ይቅትልዎሙ ። | ይህንንም በሰሙ ጊዜ ተበሳጩ ጥርሳቸውንም አፋጩ ፡ ሊገድሏቸው ወደዱ ። ምዕ ፯ ፡ ፶፬ ። | ፴፫ |
| ፴፬ | ወተንሥአ አሐዱ እምውስተ ዓውድ እምሕዝበ ፈሪሳውያን ዘስሙ ገማልያል መምህረ ኦሪት ወክቡር ውእቱ በኀበ ኵሉ ሕዝብ ወአዘዘ ያእትትዎሙ ለሐዋርያት ሕቀ እምውስተ ዓውድ ። | ከአደባባይም በሕዝቡ ሁሉ ዘንድ የከበረ የኦሪት መምህር ስሙን ገመልያል የሚሉት አንድ ፈሪሳዊ ተነሣ ሐዋርያትንም ጥቂት ያስወግዷቸው አዘዘ ምዕ ፳፪ ፫። | ፴፬ |
| ፴፭ | ወይቤሎሙ አንትሙ ሰብአ እስራኤል አድኅኑ ርእሰክሙ ወዑቁ በእንተ እሉ ሰብእ ዘከመ ትገብሩ ። | እሱ እንዲህ አላቸው እናንተ የእስራኤል ሰዎች ! ራሳችሁን አድኑ ስለ እነዚህ ሰዎችም የምታደርጉትን ዕወቁ ። | ፴፭ |
| ፴፮ | ቀዲሙኒ እምቅድመዝ መዋዕል ተንሥአ ቴዎዳስ | ቀድሞም ከዚህ ዘመን በፊት ግብፃዊው ቴዎዳስ | ፴፮ |

ዘግብፅ ወአዕበየ ርእሶ ወተለውዎ አርባዕቱ ምእት
ሰብእ ወጠፍአ ውእቱኒ ወኵሎሙ እለ አምኑ በቱ
ተዘርወ. ወኮኑ ከመ ዘኢተፈጥሩ ።
፴፯ ወእምድኅሬሁ ተንሥአ ይሁዳ ዘገሊላ በመዋዕል
ዘተጽሕፉ ሰብእ በእንተ ጸብሕት ወተለውዎ ብዙ
ኃን ሕዝብ ወሞተ ውእቱሂ ወእለ ተለውዎሂ ተዘ
ርወ. ኵሎሙ ።
፴፰ ወይእዜኒ እቤለክሙ ኅድግዎሙ ለእሉ ሰብእ ወኢት
ስሐጥዎሙ ለእመሁ ዘእምኀበ ሰብእ ዝ ምክሮሙ
ወዝ ግብሮሙ የኃልፍ ወይሠዐር ።
፴፱ ወለእመ እምኀበ እግዚአብሔር ኮነ ኢትክሉ አድኅ
ኖቶሙ ወከመ ዘምስለ እግዚአብሔር ይትበአሱ
ኢትኩኑ ።
፵ ወአሆ አበሎሙ ወጸውዕዎሙ ለሐዋርያት ወቀሠፍ
ዎሙ ወገሠፅዎሙ ኢይንግሩ እንከ በስሙ ለኢየ
ሱስ ወኅደግዎሙ ።
፵፩ ወወፅኡ እምዐውድ እንዘ ይትፌሥሑ እስመ ከፈ
ሎሙ መንፈስ ቅዱስ ከመ ያኅሥርዎሙ በእንተ
ስሙ ።
፵፪ ወኵሎ አሚረ ይፀመዱ ትምህርተ በቤተ መቅደስ
ወውስተ ቤትኒ ኢኀደጉ ነጊረ በእንተ እግዚእነ
ኢየሱስ ክርስቶስ ።

ምዕራፍ ፮ ፤
<u>ክፍል ፳ወ፬ ፡ በእንተ ሢመተ ዲያቆናት ።</u>

፩ ወውእተ አሚረ በዝኁ ሕዝብ ወግእዝዎሙ ለእለ
እምአረሚ አርድእት ለአይሁድ እስመ ይሬእይዎን
ለመበለታቲሆን እንዘ ኢይፀመዳ ኵሎ አሚረ ወያሰ
ትታ ተልእኮቶን ።
፪ ወጸውዕዎሙ ዐሠርቱ ወክልኤቱ ለኵሉ ሕዝብ ወይ
ቤልዎሙ ኢይደልወነ ከመ ንኅድግ ቃለ እግዚአብ
ሔር ወንፀመድ ማእዳተ ።
፫ ኅረዩ እምውስቴትክሙ ሰብዐተ እደወ እለ ምሉዓን
መንፈስ ቅዱስ ወጥበበ እለ ንሠይሞ ዲበ ዝ ግብር ።
፬ ወንሕነሰ ንፀመድ ጸሎተ ወመልእክተ ቃሉ ወኀብሩ
ኵሎሙ ሕዝብ ።
፭ ወሠናየ ኮነ ዝ ነገር በኀቤሆሙ ፡ ወኀረዩ እስጢፋኖ
ስሃ ብእሴ ዘምሉእ ሃይማኖተ ወመንፈስ ቅዱስ ወፊ
ልጶስ ፡ ወጰርኮሮስ ፡ ወኒቃሮና ፡ ወጢሞና ፡ ወጳር
ሜና ፡ ወኒቆላዎስ ፈላሴ ዘሀገረ አንጾኪያ ።
፮ ወአቀምዎሙ ቅድመ ሐዋርያት ወጸለዩ ወወደዩ
እደዊሆሙ ላዕሌሆሙ ።
፯ ወዐብየ ቃለ እግዚአብሔር ወበዝኁ ሕዝብ በኢየሩ
ሳሌም ፈድፋደ ወብዙኃን እምውስተ ካህናት እለ
አምኑ ።



ተነሥቶ ራሱን ከፍ ከፍ አደረገ አምላክን ነኝ አለ
አራት መቶ ሰዎችም ተከተሉት ፡ ግን እሱም ጠፋ.
ያመኑበትም ተበታተኑና እንዳልተፈጠሩ ሆኑ ።
ከሱም በኋላ ሰዎች ለግብር በተቀጠሩበት ወራት ፴፯
ገሊላዊው ይሁዳ ተነሣ ፡ እሱም ሞተ የተከተሉትም
ሁሉ ተበታተኑ ።

አሁንም እኔ ልንገራችሁ እነዚህን ሰዎች ተዉዋቸው ፴፰
አትንኳቸው ፡ ይህ ትምህርታቸው ይህ ሥራቸው
ከሰው የተገኘ ከሆነ ያልፋል ይጠፋል ።
ከእግዚአብሔር የመጣ ከሆነ ግን ልታስተዉዋቸው ፴፱
አትችሉም ፡ ግን ከእግዚአብሔር ጋር እንደሚጣላ
አትሁኑ ። ዘፍ ፳፬ ፡ ፶ ። ምዕ ፱ ፡ ፭ ።
እሺ አሰኛቸው ሐዋርያትንም ጠርተው ገርፈው እን ፵
ግዲህ ወዲህ በኢየሱስ ስም እንዳያስተምሩ ገሥ
ፀው ተዉዋቸው ። ምዕ ፳፪ ፡ ፲፱ ።
ከአደባባይም ደስ እያላቸው ወጡ ስለ ስሙ መከራ ፵፩
እንዲቀበሉ መንፈስ ቅዱስ ዓድሏቸዋልና ። ምዕ ፭ ፡
፲ - ፲፪ ። ፩ ጴጥ ፬ ፡ ፲፫ ።
ሁልጊዜም በቤተ መቅደስ ጸሎትን ያዘወትሩ ነበር ፵፪
በቤትም ስለ ጌታችን ስለ ኢየሱስ ክርስቶስ ማስተ
ማርን አልተዉም ።

ምዕራፍ ፮ ፤
<u>ክፍል ፳፬ ፡ ስለ ዲያቆናት መሾም ።</u>

ያን ጊዜ ሕዝቡ በዙ ከአረማውያን ከዕርአውያን ፩
ወገን የሆኑ አርድእት አይሁድን ነቀፏቸው ፡ ሴቶቻ
ቸውን ዘወትር ሥራ ትተው ተግባረ ፈት ሆነው ፡
ያዩዋቸው ነበርና ። ምዕ ፬ ፡ ፴፭ ።
ዐሥራ ሁለቱም ሕዝቡን ሁሉ ጠርተው እንዲህ አሏ ፪
ቸው ፡ የእግዚአብሔር ቃልን ትተን የምግብ ቤት
ሠራተኞች ልንሆን አይገባንም ።
ከመካከላችሁ መንፈስ ቅዱስ ያደረባቸውን ዕው ፫
ቀት ያላቸውን በዚህ ሥራ ላይ የምንሾማቸውን ሰዎ
ችን ምረጡ ። ዘዳግ ፩ ፡ ፲፫ ። ፩ ጢሞ ፫ ፡ ፮ - ፰ ።
እኛ ግን ጸሎትን ወንጌልን ማስተማርን ሥራ አድር ፬
ገን እንይዛለን ፡ ሕዝቡም ሁሉ ተስማሙ ።
ይህም ነገር ለነሱ ዘንድ የተወደደ ሆነ ፡ መንፈስ ፭
ቅዱስ ያደረበትን ሃይማኖቱ የቀና እስጢፋኖስን
መረጡ ፡ ፊልጶስ ፡ ጰርኮሮስ ፡ ኒቃሮና ፡ ጢሞና ፡
ጳርሜና ፡ ከአንጾኪያ ሀገር የመጣ ኒቆላዎስም አብ
ረው ተመረጡ ። ምዕ ፬ ፡ ፴፮ ።
በሐዋርያት ፊትም አቆሟቸውና ጸልየው እጃቸውን ፮
በላያቸው ጭነው ሾሟቸው ። ምዕ ፩ ፡ ፳፬ ።
የእግዚአብሔርም ቃል ከፍ ከፍ አለ ፡ በኢየሩሳሌ ፯
ምም ምእመናን በዙ ፡ ከካህናትም መካከል ያመኑ
ብዙዎች ነበሩ ። ምዕ ፲፱ ፡ ፳ ። ቈላ ፩ ፡ ፮ ።

ክፍል ፳ወ፫ ፡ በእንተ ቁመቱ ለእስጢፋኖስ ።

፰ ወእስጢፋኖስሰ ምሉአ ጸጋ እግዚአብሔር ወኃይል
ወይገብር ዐቢየ ተአምረ ወመንክረ በውስተ ሕዝብ ፤

፱ ወበ እለ ተንሥኡ እምኵራብ እንተ ስማ ሊቤርጢ
ኖን ወቀርኔዎን ወእለስክንድሬዎን ወእለሂ እምቂል
ቅያ ወእስያ ወተኃሠሥዎ ለእስጢፋኖስ ።
፲ ወስእኑ ተቃውሞቶ እስመ በጥበብ ወበመንፈስ ይት
ናገሮሙ ።
፲፩ ወእምዝ አቅፀሩ ሎቱ እደወ ሰማዕተ ሐሰት ወመሀ
ርዎሙ ከመ ይበሉ ሰማዕናሁ ለዝ ብእሲ እንዘ ይነ
ብብ ነገረ ፅርፈት ላዕለ ሙሴ ወላዕለ እግዚአብሔር ።

፲፪ ወሆከዎሙ ለሕዝብ ወለረበናት ወለጸሐፍት ወሮ
ድዎ ወሰሐብዎ ወተባጽሕዎ ኀበ ዐውድ ።

፲፫ ወአቀሙ ሎቱ ሰማዕተ ሐሰት ወይቤሉ ዝ ብእሲ
አበየ ያርምም እንዘ ይነብብ ፅርፈተ ዲበ ቤተ መቅ
ደስ ወዲበ ኦሪት ።
፲፬ ወሰማዕናሁ እንዘ ይብል ኢየሱስ ናዝራዊ ይነሥቶ
ለቤተ መቅደስ ወይሥዕር ኦሪተክሙ ዘወሀበክሙ
ሙሴ ።
፲፭ ወነጸርዎ ኵሎሙ እለ ይነብሩ ዐውደ ወርእዩ ገጾ
ከመ ገጸ መልአከ እግዚአብሔር ።

ክፍል ፳፫ ፡ ስለ እስጢፋኖስ መከሰስ ።

እስጢፋኖስም የእግዚአብሔር ኃይልና ጸጋ የመላ ፰
በት ሰው ነበር ፤ በሕዝቡም መከከል ታላላቅ ተአም
ራትና ድንቅ ሥራ ይሠራ ነበር ።
ሊቤርጢኖን ከምትባለው ምኵራብ ከቀርኔዎን ከእለ ፱
ስክንድሬዎን የተነሡ ከቂልቅያ ከእስያ የሆኑ ሰዎ
ችም ነበሩና እስጢፋኖስን ተከራከሩት ።
ግን መርታት ተሳናቸው በዕውቀት በሃይማኖት ይከ ፲
ራከራቸው ነበርና ። ሉቃ ፳፩ ፡ ፲፭ ።
ከዚህ በኋላ የሐሰት ምስክሮች የሚሆኑ ሰዎች አስነ ፲፩
ሡበት ፤ ይህን ሰው በሙሴና በእግዚአብሔር ላይ
የስድብ ቃል ሲናገር ሰምተነዋል እንዲሉ ሐሰት አስ
ተማሯቸው ። ማቴ ፳፯ ፡ ፰ ።
ሕዝቡንና ሽማግሌዎችን ጸሐፊዎችንም አነሣሡአ ፲፪
ቸው አዳርሱን ብለው ከበው እየጐተቱ ወደ አደባ
ባይ ወሰዱት ።
የሐሰት ምስክሮች አቆሙበት እነሱንም እንዲህ አሉ ፡ ፲፫
ይህ ሰው በቤተ መቅደስ ላይ ፡ በኦሪትም ላይ ስድ
ብን ሲናገር ተው ብንለው እንቢ አለ ። ኤር ፳፯ ፡ ፲፩ ።
የናዝሬቱ ኢየሱስ ቤተ መቅደሳችሁን ያፈርሰዋል ፡ ፲፬
ሙሴ የሰጣችሁ ኦሪታችሁን ይሽራል ሲል ሰም
ተነዋል ።
በአደባባይ ተቀምጠው የነበሩት ሁሉ ተመለከቱት ፲፭
ፊቱንም የእግዚአብሔርን መልአክ ፊት ሆኖ አዩት ።
ዘዳን ፲ ፡ ፯ ። ማቴ ፲፯ ፡ ፪ ። ራእ ዮሐ ፲ ፡ ፩ ።

ምዕራፍ ፯ ፡

ክፍል ፳ወ፬ ፡ ነገር ዘተናገረ ለሊቀ ካህናት ።

፩ ወይቤሎ ሊቀ ካህናት አማንኑ ከመዝ ትቤ ።
፪ ወይቤ ስምዑ አኃዊነ ወአበዊነ አምላከ ስብሐት
አስተርአዮ ለአቡነ አብርሃም እንዘ ሀሎ በማእከለ
አፍላግ ዘሶርያ ዘእንበለ ይፍልስ ካራን ።

፫ ወይቤሎ ፃእ እምብሔርከ ወተፈለጥ እምአዝማዲከ
ወነዓ ውስተ ብሔር ዘአነ አርእየከ ።
፬ ወእምዝ ወፅአ እምከላውዴዎን ነበረ ውስተ ካራን
ወእምዝ መዊቶ አቡሁ አፍለሶ ውስተ ዛ ምድር ኀበ
ሀለውክሙ አንትሙ ይእዜ ትነብሩ ።
፭ ወኢወሀቦ በውስቴታ ርስቶ ወኢመጠነ ምክያደ
እግር ወኢምስጋረ እግር ወባሕቱ አሰፈዎ ከመ ይኩ
ንና ውእቱ ወዘርኡ እምድኅሬሁ እንዘ አልቦ ውሉድ
ይእተ አሚረ ።

፮ ወከመዝ ይቤሎ እግዚአብሔር ሀለወ ደቂቅከ ይነ
ብሩ ፈላስያነ ብሔረ ነኪር ወይቀንይዎሙ ግብፅ
ወያሐምምዎሙ አርባዕተ ምእተ ዓመተ ።

ምዕራፍ ፯ ፡

ክፍል ፳፬ ፡ ለካህናት አለቆች ስለ ተናገረው ታሪክ ።

ሊቀ ካህናቱም እውነት ነው እንዲህ ብለሃልን አለው ። ፩
እሱም እንዲህ አለ ፡ ወንድሞቻችንና አባቶቻችን ! ፪
ስሙ ወደ ካራን ከመምጣቱ አስቀድሞ በሶርያ ወን
ዞች መካከል ሳለ ለአብርሃም የክብር ባለቤት እግዚ
አብሔር ተገለጠለት ። ዘፍ ፲፩ ፡ ፴፩ ። ፲፭ ፡ ፯ ።
ከገርህ ውጣ ከዘመዶችህ ተለይ እኔ ወደ ማሳይህ ፫
ሀገርም ና አለው ። ዘፍ ፲፪ ፡ ፩ - ፲፪ ።
ከዚህ በኋላ ከከላውዴዎን ወጥቶ በካራን ተቀመጠ ፬
አባቱም ከሞተ በኋላ ዛሬ እናንተ ወደ አላችሁበት
ወደዚች አገር አመጣው ። ዘፍ ፲፩ ፡ ፴፩ ። ዕብ ፲፩ ፡ ፰ ።
በውስጢም አንድ ጫማ ወይም አንድ እርምጃ እን ፭
ኳን ርስትህ ነው ብሎ አልሰጠውም ፤ ነገር ግን ያን
ጊዜ ልጅ እንኳ ሳይኖረው ራሱ ከሱም በኋላ ዘሩ
እንደሚገዛለት ተስፋ ሰጠው እንጂ ። ዘፍ ፲፪ ፡ ፯ ።
ዘዳግ ፮ ፡ ፲ ። ነህ ፱ ፡ ፰ ።
እግዚአብሔርም እንዲህ አለው ፡ ልጆችህ በባዕድ ፮
አገር መጻተኞች ሆነው ይኖራሉ ፤ ግብፃውያን ይገ
ዟቸዋል አራት መቶ ዓመትም መከራ ያጸኑባቸዋል ።
ዘፍ ፲፭ ፡ ፲፫ ። ዘፀ ፲፪ ፡ ፵ ። ገላ ፫ ፡ ፲፪ ።

፯ ወለሕዝብሰ እለ ይቀንይዎሙ አነ እኴንኖሙ ይቤ እግዚአብሔር ወእምዝ ይወፅኡ ዝየ ወያመልኩኒ በዝ ብሔር ።

፰ ወወሀበ ሥርዓተ ግዝረት ወእምዝ ወለዶ ለይስሐቅ ወገዘሮ አመ ሳምንት ዕለት ወከማሁ ይስሐቅኒ ለያዕቆብ ወያዕቆብኒ ለዐሠርቱ ወክልኤቱ አበው ቀደምት።

## ክፍል ፻ወ፯ ፡ በእንተ ዮሴፍ ።

፱ ወአበዊነሂ ቀደምት ቀንኡ ላዕለ ዮሴፍ ወሤጥዎ ለብሔረ ግብፅ ወሀሎ እግዚአብሔር ምስሌሁ ።

፲ ወአድኅኖ እምኵሉ ምንዳቤሁ ወወሀቦ ሞገሰ ወጥበበ በቅድመ ፈርዖን ንጉሠ ግብፅ ወሤሞ ላዕለ ኵሉ ግብፅ ወሊመገበ ላዕለ ኵሉ ቤቱ ።

፲፩ ወመጽአ ረኃብ ለብሔረ ግብፅ ወበከነዓን ዐቢይ ሕማም ወኃጥኡ ዘይሴሰዩ አበዊነ ።

፲፪ ወሰምዐ ያዕቆብ ከመበ እክል በብሔረ ግብፅ ወፈነ ዎሙ ለአበዊነ ቅድመ ።

፲፫ ወሶበ ገብኡ ዳግመ ለግብፅ አፍለጦሙ በነፍሰቱ ዮሴፍ ለአኃዊሁ ወአእመሮሙ ፈርዖንሂ ለአዝማደ ዮሴፍ ።

፲፬ ወለአከ ዮሴፍ ወጼውዖሙ ለአቡሁ ወለኵሎሙ አዝማዲሁ ወከነ ፍቅዶሙ ሰብዓ ወኃምስቱ ነፍስ ።

## ክፍል ፻ወ፰ ፡ በእንተ ርደተ ያዕቆብ ውስተ ግብፅ ።

፲፭ ወወረደ ያዕቆብ ብሔረ ግብፅ ወሞተ ውእቱ ፡ ወአበዊነሂ ።

፲፮ ወአፍለስዎሙ ኀበ ሴኬም ወተቀብሩ ውስተ መቃብር ዘተሣየጠ አብርሃም በወርቁ እምኀበ ደቂቀ ኤሞር በሴኬም ።

፲፯ ወአመ በጽሐ ዕድሚሁ ዘአሰፈዎ እግዚአብሔር ለአብርሃም በመሐላ በዝኁ ሕዝብ ወመልኡ ብሔረ ግብፅ ።

፲፰ እስከ አመ ነግሠ ካልእ ንጉሥ ለብሔረ ግብፅ ዘኢየአምሮ ለዮሴፍ ።

፲፱ ወውእቱ ተጠቢቦ ሣቀዮሙ ወአሕመሞሙ ለአበዊነ ወአዘዘ ይቅትሉ ኵሎ እጓለ ተባዕት ።

## ክፍል ፻ወ፱ ፡ በእንተ ሙሴ ።

፳ ወውእተ አሚረ ተወልደ ሙሴ ወከነ ሠናየ በቅድመ እግዚአብሔር ወኃፀንዎ ሠለስተ አውራኀ በቤተ አቡሁ ።



ደግሞም እግዚአብሔር እንዲህ አለ ፡ በሚገዙቸው ወገኖች እኔ እፈርድባቸዋለሁ ፡ ከዚህ በኋላ ወደ ዚህ መጥተው በዚህ ቦታ ያመልኩኛል ። ፯

የግዝረትን ሥርዓት ሰጠው ከዚህ በኋላ ይስሐቅን በወለደ ጊዜ በስምንተኛው ቀን ገዘረው እንዲሁ ይስ ሐቅም ያዕቆብን ገዘረ ፡ ያዕቆብም ዐሥራ ሁለቱን ነገድ ገዘረ ። ዘፍ ፲፯ ፡ ፲ ። ዘፍ ፳፩ ፡ ፬ - ፬ ። ዘፍ ፳፭ ፡ ፳፯ ። ገላ ፫ ፡ ፲፭ - ፲፯ ። ፰

## ክፍል ፻፯ ፡ ስለ ዮሴፍ ።

የቀደሙ አባቶቻችንም በዮሴፍ ላይ ቀንተው ወደ ግብፅ አገር ሸጡት ፡ እግዚአብሔር ግን አብሮት ነበር ። ዘፍ ፴፯ ፡ ፯ - ፳፰ ። መዝ ፻፭ ፡ ፲፯ ። ፱

ከመከራው ሁሉ አዳነው ፡ በግብፅ ንጉሥ በፈርዖን ፊትም ዕውቀትን መወደድን ሰጠው ፡ በቤቱ ሁሉ ላይም ሾመው ። መዝ ፻፭ ፲፯ - ፳ ። ዘፍ ፴፱ ፡ ፪ ። ፲

በግብፅ ረኃብ መጣ ፡ በከነዓንም ታላቅ ጭንቅ ሆነ አባቶቻችንም የሚበሉት አጡ ። ፲፩

ያዕቆብም በግብፅ እህል እንዳለ፤ሰምቶ አባቶቻችንን አስቀድሞ ላካቸው ። ዘፍ ፵፪ ፡ ፩ ። ፲፪

ወደ ግብፅም እንደገና፤በተመለሱ ጊዜ ዮሴፍ ለወ ንድሞቹ በሰውነቱ (በግዙርነቱ) እንዲያውቁት አደ ረገ ፡ ፈርዖንም የዮሴፍን ዘመዶች አወቃቸው ። ዘፍ ፵፭ ፡ ፩ - ፬ ። ፲፫

ዮሴፍም አባቱንና ዘመዶቹን ሁሉ እንዲጠሩአቸው ላከ ፡ ቍጥራቸውም ሰባ አምስት ነፍስ ነበር ። ዘፍ ፵፭ ፡ ፱ - ፲ ። ፲፬

## ክፍል ፻፰ ፡ ያዕቆብ ወደ ግብፅ ስለ መውረዱ ።

ያዕቆብ ወደ ግብፅ ወረደ እሱም ሞተ ፡ አባቶቻች ንም ሞቱ ። ዘፍ ፵፯ ፡ ፩ ። ፵፱ ፡ ፴፫ ። ዘፀ ፩ ፡ ፮ ። ፲፭

ወደ ሴኬምም ወሰዱአቸውና አብርሃም ከኤሞር ልጆች በወርቁ በገዛው መቃብር በሴኬም ተቀበሩ ። ዘፍ ፳፫ ፡ ፲፮ - ፲፯ ። ኢያ ፳፬ ፡ ፴፪ ። ፲፮

እግዚአብሔርም ለአብርሃም በመሐላ የሰጠው ቀጠሮ በደረሰ ጊዜ ፡ እስራኤል በዙ ግብፅንም መሉ ። ዘፍ ፩ ፡ ፯ ። ፲፯

ዮሴፍ የማያውቀው ሌላ ንጉሥ በግብፅ እስከ ነገሠ ድረስ ። ፲፰

እሱም ተጠቦ አባቶቻችንን መከራ አጸናባቸው አስ ጨነቃቸው ወንድ ልጅንም ሁሉ እንዲገድሉ አዘዘ። ዘፀ ፩ ፡ ፳፪ ። ፲፱

## ክፍል ፻፱ ፡ ስለ ሙሴ ።

ያን ጊዜ ሙሴ ተወለደ ፡ በእግዚአብሔር ፊትም የተወደደ ሆነ ፡ ሦስት ወር ያህልም በአባቱ ቤት አሳደጉት ። ዘፀ ፪ ፡ ፪ ። ዕብ ፲፩ ፡ ፳፫ ። ፳

፳፩ ወእምዝ ገደፍዎ ውስተ ባሕር ወአንሥአቶ ወለተ ፈርዖን ወኀፀነቶ ወረሰየቶ ወልደ ።
፳፪ ወተምህረ ሙሴ ተግሣፀ ወኵሎ ጥበበ ግብፅ ወኮነ ጽኑዐ በቃሉ ወበምግባሩ ።

### ክፍል ፴ ፡ በእንተ ዘከመ ሐወጾሙ ሙሴ ለአኃዊሁ ።

፳፫ ወአመ ተፈጸመ አርብዓ ዓመት ሐለየ በልቡ የሐውፆሙ ለአኃዊሁ ደቂቀ እስራኤል ።
፳፬ ወረከበ፡አሐደ ግብፃዊ እምውስቴቶሙ እንዘ ይገፍዖ ለዕብራዊ፤ ወተበቀለ ሎቱ ለውእቱ ዘተገፍዐ ወቀተሎ ለግብጻዊ ወደፈኖ ውስተ ኆፃ ።
፳፭ ወመሰሎ ዘየአምሩ አኃዊሁ ከመ በእዴሁ ይሁቦሙ እግዚአብሔር መድኃኒተ ወእሙንቱሰ ኢለበዉ ።

፳፮ ወበሳኒታ ረከበ ክልኤተ እምውስቴቶሙ እንዘ ይትበአሱ ወፈቀደ ይዕቀርሙ ወይቤሎሙ ናሁ አንትሙሰ አኃው አንትሙ ለምንት ትትዓመፁ በበይናቲክሙ ።
፳፯ ወይቤሎ ዝኩ ዘይዔምፆ ለካልኡ መኑ ሤመከ መልአከ ወመኰንነ ላዕሌነ ።
፳፰ ወሚመ ትፈቅድኑ ትቅትለኒ ኪያየኒ በከመ ቀተልከ ትማልም ለግብፃዊ ።
፳፱ ወበእንተዝ ነገር ተኃጥአ ሙሴ ወነበረ ፈላሴ ብሔረ ምድያም ወወለደ በህየ ክልኤተ ደቂቀ ።

### ክፍል ፴ወ፩ በእንተ ነጽሮተ ሙሴ መልአከ እግዚአብሔር ።

፴ ወተፈጺሞ አርብዓ ዓመት አስተርአዮ በገዳም በደብረ ሲና መልአከ እግዚአብሔር በነደ እሳት ።

፴፩ ወርእዮ ሙሴ አንከረ ግርማሁ ወቀርበ ይጠይቆ ወነበቦ እግዚአብሔር ወይቤሎ ።
፴፪ አነ ውእቱ እግዚአብሔር አምላከ አበዊከ አምላከ አብርሃም ፣ ወአምላከ ይስሐቅ፡ ወአምላከ ያዕቆብ ፣ ወርእደ ሙሴ ወስእነ ጠይቆ ።
፴፫ ወይቤሎ እግዚአብሔር ፍታሕ አሣእኒከ እምእገሪከ እስመ ምድር ኀበ ትከይድ ቅድስት ይእቲ ።
፴፬ ርእየ ርኢኩ ሕማሞሙ ለሕዝብየ ወሰማዕኩ ገዐሮሙ ወወረድኩ ከመ እድኅኖሙ ወይእዜኒ ነዓ እፈኑከ ብሔረ ግብጽ ።

### ክፍል ፴ወ፪ ፡ በእንተ ሙሴ ።

፴፭ ለውእቱ ሙሴ ዘክሕድዎ ወይቤልዎ መኑ ሤመከ መልአከ ወመኰንነ ላዕሌነ ኪያሁ ፈነወ እግዚአብሔር መልአከ ወመድኅነ በእደ መልአኩ ዘአስተርአዮ በኀበ ዕፀ ጳጦስ ።

ከዚህም በኋላ ወደ ባሕር ጣሉት ግን የፈርዖን ልጅ አንሥታ አሳድጋ ልጅ አደረገችው ። ዘፀ ፪ ፡ ፲ ። ፳፩
ሙሴም ምክርን የግብፅንም ጥበብ ሁሉ ተማረ በሚናገረው በሚሠራውም ሁሉ ብርቱ ሆነ ። ፳፪

### ክፍል ፴ ፡ ሙሴ ወንድሞቹን እንደ ጐበኛቸው ።

አርባ ዓመት ሲመላውም ወንድሞቹን የእስራኤልን ልጆች ሊጐበኛቸው አሰበ ። ዘፀ ፪ ፣ ፲፩ ። ፳፫
አንድ ግብፃዊ ዕብራዊውን ሲበድለው አገኘና በዚያ ለተበደለው ረድቶ ግብፃዊውን ገድሎ በአሸዋ ውስጥ ቀበረው ። ፳፬
ወንድሞቹም እግዚአብሔር በእጁ ድኅነትን እንደ ሚያደርግላቸው የሚያውቁ መስሎት ነበር ፣ እነሱ ግን አላወቁም ። ፳፭
በማግሥቱም ከመከከላቸው ሁለት ሰዎች እርስ በርሳቸው ሲጣሉ አገኘ ፣ ሊያስታርቃቸውም ፈልጎ እነሆ እናንተማ ወንድማማቾች ናችሁ ፣ እርስ በርሳችሁ ለምን ትጣላላችሁ ? አላቸው ። ፳፮
ያ ጓደኛውን የሚበድበውም በእኛ ላይ ዳኛና ፈራጅ አድርጎ ማን ሾመህ ? አለው ። ፳፯
ወይስ ትናንትና ግብፃዊውን እንደ ገደልከው እኔንም ልትገድለኝ ትፈልጋለህን ? ። ፳፰
ስለዚህም ነገር ሙሴ ኰብልሎ በምድያም አገር ስደተኛ ሆኖ ኖረ ፣ በዚያም ሁለት ልጆችን ወለደ ። ዘፀ ፪ ፣ ፲፭ ። ፳፱

### ክፍል ፴፩ ፡ ሙሴ የእግዚአብሔርን መልአክ ስለ ማየቱ ።

አርባ ዓመት ሲሆነውም የእግዚአብሔር መልአክ በበረኻ በደብረ ሲና በእሳት ነበልባል ታየው ። ዘፀ ፫ ፡ ፪ ። ዘዳግ ፴፫ ፡ ፲፮ ። ፴
ሙሴም ግርማውን አይቶ አደነቀ ፣ ሊያስተውለውም ቀረበ ፡ እግዚአብሔር እንዲህ ብሎ ተናገረው ። ፴፩
የአባቶችህ ፈጣሪ የአብርሃም አምላክ ፣ የይስሐቅ አምላክ ፡ የያዕቆብ አምላክ እግዚአብሔር እኔ ነኝ ፣ ሙሴም ደነገጠና ማስተዋል ተሳነው ። ዘፀ ፫ ፣ ፮ ። ፴፪
እግዚአብሔርም እንዲህ አለው ፡ ጫማህን ከእግርህ አውልቅ የቆምክባት ምድር የተቀደሰች ናትና ። ፴፫
የወገኖቼን መከራ ማየትን አይቻለሁ ጩኸታቸውንም ሰምቻለሁ ላድናቸውም ወርጃለሁ አሁንም ና ወደ ግብፅ ልላክህ ። ፴፬

### ክፍል ፴፪ ፣ ሙሴ ወደ ግብፅ ስለ መላኩ ።

የከዱትን በእኛ ላይ ዳኛና ፈራጅ ማን አድርጎሃል ያሉትን ያንን ሙሴ በዕፀ ጳጦስ አጠገብ በታየው በመልአኩ ቃል ጠርቶ እሱን አዳኝና መልእክተኛ አድርጎ እግዚአብሔር ላከው ። ዘፀ ፪ ፣ ፲፬ ። ፴፭

፰ በኑ እንጋ ንሕነ ዘከመ ይጸርፉ ላዕሌነ እለ ይጸርፉ
ወይትሐዘቡነ ከመ ንሕነ ንብል ንግበር እኩየ ከመ
ንርከብ ሠናየ ወሎሙሰ ጽኑሕ ደይኖሙ ።

፱ ምንተ እንከ ንብል ናሁ ወዳእነ ግእዝናሆሙ ለአይ
ሁዳዊ ወለአረማዊ እስመ ኵሎሙ ስሕቱ ።

## ክፍል ፲ወ፫ ፡ በእንተ ተኀጥአተ ጻድቅ ወጠቢብ ።

፲ በከመ ይብል መጽሐፍ አልቦ ጻድቅ ወአልቦ ጠቢብ።

፲፩ ወአልበ ዘየኀሥሥ ለእግዚአብሔር ።
፲፪ ኵሉ ዐረየ ወኀቡረ ዐለወ ፡ አልቦ ዘይገብራ ለሠና
ይት አልቦ ወኢአሐዱ ።
፲፫ ከመ መቃብር ክሡት ጐራዒቶሙ ወጓሕሉዉ በል
ሳናቲሆሙ ።
፲፬ ኆምዘ አርዌ ምድር ታሕተ ከናፍሪሆሙ መሪር አፉ
ሆሙ ወምሉእ መርገመ ።
፲፭ በሊሕ እገሪሆሙ ለክዒወ ደም ።
፲፮ ኀሣር ወቅጥቃጤ ውስተ ፍኖቶሙ ።
፲፯ ወኢየአምርዋ ለፍኖተ ሰላም ።
፲፰ ወአልበ ፍርሃተ እግዚአብሔር ቅድመ አዕይንቲ
ሆሙ ።

## ክፍል ፲ወ፬ ፡ በእንተ እለ የዐቅቡ ኦሪት ።

፲፱ ነአምር ከመ ኵሉ ዘይብል ኦሪት ለእለ ውስተ ኦሪት
ይቤሎሙ ከመ ይትፈጸም ኵሉ አፍ ወይኩን ግሩረ
ኵሉ ዓለም ለእግዚአብሔር ።

፳ እስመ ኢይጸድቅ ኵሉ ዘነፍስ በገቢረ ሕገገ ኦሪት
በቅድመ እግዚአብሔር ፡ እስመ እምኦሪት ተዐው
ቀት ኃጢአት ።
፳፩ ይእዜሰኬ አስተርአየት ጽድቀ እግዚአብሔር እንዘ
ኢይትገበር ሕገገ ኦሪት ።
፳፪ ኦሪት ወነቢያት ኮንዎ ሰማዕተ ከመ በአሚን በኢየ
ሱስ ክርስቶስ ይጸድቁ በኀበ እግዚአብሔር ኵሎሙ
እለ የአምኑ ቦቱ ።
፳፫ ኢፈለጠ ወኢሌለየ እስመ ኵሎሙ አበሱ ወኄገዩ
ወኀደጉ ስብሐተ እግዚአብሔር ።

፳፬ ወጽድቅሰኬ በከንቱ ኮነ በጸጋ ዚአሁ ረከቡ ሕይ
ወተ በኢየሱስ ክርስቶስ ።

፳፭ እስመ ወድአ እግዚአብሔር ወገብሮ ሥርየተ ለአ
ሚን በደሙ ከመ ያርኢ ጽድቆ በላዕለ እለ አበሱ
እምትካት ።
፳፮ በትዕግሥቱ ለእግዚአብሔር ወበአሆ ብሂሎቱ ከመ

በውኑ እኛ መልካም ነገር እንድናገኝ፡ ክፉ ነገር ፰
እናድርግ እንደምንል አስመስለው የሚጠረጥሩን
የሚነቅፉን ሰዎች በእኛ ላይ እንደሚናገሩት ነንን? ለኑ
ሱስ ቅጣታቸው ተዘጋጅቶላቸዋል ። ምዕ ፯ ፩-፪ ።
አይሁዳዊዉንም አረማዊዉንም ነቅፈናቸዋል ፡ እን ፱
ግዲህ ምን እንላለን ? ሁሉም በድለዋልና ።

## ክፍል ፲፫ ፡ ብልህና እውነተኛ ሰው ስለ መታጣቱ ።

መጽሐፍ እንዲህ እንዳለ "ጻድቅ የለም አዋቂም ፲
የለም ።
እግዚአብሔርንም የሚሻው የለም ። መዝ ፲፬ ፩-፺፫ ፬ ። ፲፩
ሁሉ ተባብሮ በደለ መልካም ነገርን የሚያደርጋት ፲፪
የለም አይገኝም አንድ ስንኳን ቢሆን ።
ጉሮሮአቸው እንደ ተከፈተ መቃብር ነው፡ በአንደበ ፲፫
ታቸው ሸነገሉ ። መዝ ፭ ፱ ። ፻፵ ፫ ።
ከከንፈራቸው ውስጥ የእባብ መርዝ አለ ፡ አፋቸው ፲፬
መራራ ነው መርገምንም የተመላ ነው ። መዝ ፲ ፯ ።
እግራቸው ደምን ለማፍሰስ ፈጣን ነው ። ኢሳ ፶፱ ፯ ። ፲፭
በመንገዳቸው ውርደት መጕሳላት አለ ። ፲፮
የሰላምን መንገድ አያውቋትም ። ፲፯
በፊታቸው እግዚአብሔርን መፍራት የለም „ ። ዘፍጥ ፲፰
፳ ፲፩ ። መዝ ፴፮ ፩ ። ሉቃ ፳፫ ፵ ።

## ክፍል ፲፬ ፡ ኦሪትን ስለሚጠብቁ ።

ኦሪት የሚናገረው ሁሉ በኦሪት ላሉት እንደሆነ እና ፲፱
ውቃለን ፡ አንደበት ሁሉ ምላሽ እንዲያጣ ፍጥረት
ሁሉ ለእግዚአብሔር እንዲገዛ ነግሯቸዋል ። ሕዝ ፲፮
፷፫ ። ምዕ ፪ ፲፪ ። ገላ ፫ ፳፪ ።
ሰው ሁሉ የኦሪትን ሕግ በመፈጸም በእግዚአብሔር ፳
ዘንድ አይጸድቅምና ከኦሪት የተነሣ ኃጢአት ታው
ቃለችና ። መዝ ፻፵፫ ፪ ። ገላ ፪ ፲፮ ።
አሁንማ የኦሪት ሕግ ሳይሠራ የእግዚአብሔር ቸር ፳፩
ነት ተገለጠች ።
ያመኑበት ሁሉ ኢየሱስ ክርስቶስን በማመን በእግ ፳፪
ዚአብሔር ዘንድ እንደሚጸድቁ ኦሪትና ነቢያት መሰ
ከሩለት ። ግብ ፲ ፵፫ ።
አልለየም አልነጠልም ሁሉም ፈጽመው በድለዋልና ፳፫
እግዚአብሔርንም ማመስገን ትተዋልና ። ቍ ፱ ።
፩ ነገ ፰ ፵፮ ። ገላ ፫ ፳፪-፳፫ ።
ጽድቅ ግን ያለዋጋ በርሱ ቸርነት ተገኘ በኢየሱስ ፳፬
ክርስቶስ ሕይወትን አገኙ ። ማቴ ፳ ፳፰ ። ዕብ ፱ ፲፪ ፤
፩ ጴጥ ፩ ፲፰-፲፱ ።
እግዚአብሔር በደሙ ማመንን መታረቂያ አደርጎታ ፳፭
ልና ከጥንት ጀምሮ በበደሉት ላይ ቸርነቱ ይገለጥ
ዘንድ ። ዘሌዋ ፲፮ ፲፪-፲፭ ። ኢሳ ፶፫ ፲፩ ።
እርሱ ቸር እንደሆነ ያመኑበትንም በኢየሱስ በማ ፳፮

ያእምርዎ ዮም ከመ ጻድቅ ውእቱ ወያጸድቆሙ
ለእለ የአምኑ በአሚን በኢየሱስ ።

## ክፍል ፲ወ፫ ፡ በእንተ እለ ይትሜክሑ ።

፳፯ በምንትኑ እንከ ይትሜክሑ ወበአይኑ ሕግ ይገብሩ
አልቦ በዕድ ሕግ ዘእንበለ አሚን ።
፳፰ እስመ ነአምር ከመ ይጸድቅ ሰብእ በአሚን እንዘ
ኢይገብር ሕገገ ኦሪት ።
፳፱ ቦኑ ለባሕቲቶሙ ለአይሁድ እግዚአብሔር ፡ አኮኑ
ለሕዝብኒ ወለአሕዛብኒ ።

፴ እስመ አሐዱ ውእቱ እግዚአብሔር ዘያጸድቆ ለግ
ዙር በአሚን ።
፴፩ ወለዘኒ ቈላፍ በአሚን ዳእሙ ያጸድቆ ፡ ሰዐርነሁ
እንከ ሕገገ ኦሪት በእንተ አሚን ሐሰ ፡ አኮ ዘንስዕር
ሕገ አላ ንሠርዕ ።

ምዕራፍ ፬ ፡

## ክፍል ፲ወ፬ ፡ በእንተ አብርሃም ።

፩ ምንተ እንከ ንብል በእንተ አብርሃም አቡሆሙ ለቀ
ደምት ረከበኑ ዘንተ በምግባረ ሥጋ ።
፪ ሶበሰኬ አብርሃም በምግባሩ ጸድቀ እምከኖ ምዝጋና
ወአኮ ለመንገለ እግዚአብሔር ።

፫ ወእፎኑመ ይብል መጽሐፍ አምነ አብርሃም በእግዚ
አብሔር ወኮኖ ጽድቀ ።

፬ ወዘሰ ተቀንየ ኢይከውኖ ዐስበ ከመ ዘጸገውዎ አላ
ከመ ዘይደልዎ ።

፭ ወዘሰ ኢተቀንየ ለእመ ተአመነ በዘያጸድቆ ለኃጥእ
ይትኌለቆ ጽድቀ አሚኖቱ ።

## ክፍል ፲ወ፭ በእንተ ብፁዓን ።

፮ በከመ ነገረ ዳዊት በዘያበፅዕ ሰብአ ወበዘኒ ይትኌ
ለቆ ጽድቀ በኀበ እግዚአብሔር እንዘ ኢይገብር
ሕገገ ኦሪት ።
፯ ወይቤ ብፁዓን እለ ተኃድገ ሎሙ ኃጢአቶሙ ።

፰ ወብፁዕ ብእሲ ዘኢኈለቈ ሎቱ እግዚአብሔር
ጌጋዮ ።
፱ ምንተ እንከ ገቢሮሙ ያበፅዑ ዘተገዝረኑ ዳእሙ ያበ
ፅዕ ርእሶ ወቈላፍሰ አልቦኑ ፍኖት ኀበ ያበፅዕ ፡ አኮኑ
ይቤ መጽሐፍ ጸድቀ አብርሃም ወአብፅዐ ርእሶ ።

መን እንደሚያጸድቃቸው የእግዚአብሔርን ታጋሽነ
ቱን ቸርነቱን ዛሬ ያውቁ ዘንድ ።

## ክፍል ፲፫ ፡ ስለ ሚመኩ ።

እንግዲህ በምን ይመካሉ የትኛውስ ሕግ ይፈጽማሉ ፳፯
ያለ ሃይማኖት ሕግ የለም ፡ ፩ ቆሮ ፩ ፳፱-፴፫ ።
ሰው የኦሪትን ሥራ ሳይሠራ በሃይማኖት እንዲከብር ፳፰
እናውቃለንና ። ገላ ፪ ፲፮-፳፩ ።
በውኑ እግዚአብሔር ለአይሁድ ለብቻቸው ነውን ? ፳፱
ለሕዝብም ለአሕዛብም አይደለምን ? ። ሚል ፪ ፲ ።
፩ ቆሮ ፲፪ ፮ ።
የተገዘረውን በሃይማኖት የሚያከብረው እሱ አንዱ ፴
እግዚአብሔር ነውና ። ምዕ ፬ ፲፩-፲፪ ።
ያልተገዘረውንም በሃይማኖት ብቻ ያከብረዋል ፡ እን ፴፩
ግዲህ ስለ ሃይማኖት ኦሪትን ሻርን? አልሻርንም ሕግን
የምንሽር አይደለም እናጸናለን እንጂ ። ምዕ ፰ ፬ ።

ምዕራፍ ፬ ።

## ክፍል ፲፬ ፡ ስለ አብርሃም ።

እንግዲህ ስለ ደጋጎቹ አባት ስለ አብርሃም ምን እንላ ፩
ለን ? በሥጋ ሥራ ይህን (አባትነትን) አግኝቷልን ? ።
አብርሃም በሥራው ክብሮስ ቢሆን በተመሰገነ ነበር ፡ ፪
ከእዚግዚአብሔር የተደረገለት ነው ባልተባለም
ነበር ።
መጽሐፍ አብርሃም በእግዚአብሔር አመነ ፡ ጽድቅ ፫
ሆኖ ተቈጠረለት እንደምን ይላል ? ። ዘፍ ፲፭ ፮ ፡ ገላ
፫ ፮ ። ያዕ ፪ ፳፫ ።
ያገለገለ ግን ዋጋው እንደሚገባው እንጂ በለጋስነት ፬
እንደሰጡት አይቈጠርበትም ። ምዕ ፲፩ ፮ ማቴ
፳፩ ፲፬ ።
ያላገለገለ ግን ኃጢአተኛውን በሚያጸድቀው ካመነ ፭
ማመኑ ጽድቅ ሆኖ ይቈጠርለታል ። ኢያ ፳፬ ፪ ።
ግብ ሐዋ ፲፫ ፴፱ ። ምዕ ፫ ፳፰ ።

## ክፍል ፲፭ ፡ ስለ ብፁዓን ።

ዳዊት ሰውን ብፁዕ ሲል የኦሪትንም ሕግ ሳይፈጽም ፮
በእግዚአብሔር ዘንድ ጽድቅ ሆኖ እንደሚቈጠርለት
ሲያስረዳ እንደተናገረ ።
እንዲህ ብሎአል ፡ "ኃጢአታቸው የተሠረየላቸው ፯
ብፁዓን ናቸው„ ። መዝ ፴፪ ፩-፪ ።
እግዚአብሔርም በደሉን ያላሰበበት ሰው ብፁዕ ነው ። ፰

እንግዲህ ምን ሠርተው ራሳቸውን ያስመሰግናሉ የተ ፱
ገዘረ ብቻ ራሱን ብፁዕ ያሰኛልን ? ያልተገዘረሳ ራሱን
ብፁዕ የሚያሰኝበት መንገድ የለውምን ? መጽሐፍ
አብርሃም ከበረ ራሱንም አስመሰገነ ይል የለምን ? ።

፲ ወማእዜኑ ጸድቀ አብርሃም ትገዚሮኑ ወሚመ ዘእን
በለ ይትገዘር ፡ አኮኬ ተገዚሮ አላ ዘእንበለ ይትገዘር ።
፲፩ ወግዝረትሰ ማዕተበ ጽድቅ ትኩኖ ወሀቦ ኪያሃ
ትእምርተ ከመ ይትዐወቅ በላዕሌሁ ከመ በአሚን
አጽደቆ እግዚአብሔር ለአብርሃም እንዘ ኢኮነ ግዙረ
ውእተ ዕለተ ፡ ከመ ይኩን አባሆሙ ለኵሎሙ ለእለ
የአምኑ ዘእንበለ ይትገዘሩ ከመ ያእምሩ ከመ በአ
ሚን ይጸድቁ እሙንቱሂ ከመ ጸድቀ አብርሃም
በአሚን ።
፲፪ ወከመ ይኩን አባሆሙ ለግዙራን ፡ ወአኮ ለግዙራን
ለባሕቲቶሙ ፡ ወለእለሂ ዓዲ ይትልዉ አሰረ ሃይማ
ኖቱ ለአቡነ አብርሃም እንዘ ኢኮኑ ግዙራነ በከመ
ውእቱ አቡነ አብርሃም አምነ እንዘ ቈላፍ ውእቱ ።

ክፍል ፲ወ፰ ፡ በእንተ ተስፋ አብርሃም ወዘርኡ ።

፲፫ ወአኮ በእንተ ሕገገ ኦሪት ዘረከበ ተስፋ አብርሃም
ወዘርኡ ከመ ይረስ ዓለመ አላ ዳእሙ ረከበ ዘንተ
በጽድቀ ሃይማኖቱ በቃለ እግዚአብሔር ወአሚን
ቦቱ ።
፲፬ ሶበሰኬ ዘገብረ ዳእሙ ሕገገ ኦሪት ይነሥእ ተስፋ
ወይወርስ ዓለመ እምኢበቀኖ ለአብርሃም አሚኖቱ
ወእምኢረከበ ተስፋሁ ።
፲፭ እስመ ሕገገ ኦሪት መቅሠፍተ ያመጽእ ዲበ ዘሀለዎ
ወኀበ አልቦ ኦሪት ወኢሕግ አልቦ አበሳ ወኃጢአት ።
፲፮ ወበእንተዝ በአሚን ረሰየ እግዚአብሔር ጻዲቀ ከመ
ይኩን እሙነ ዘአሰፈዎ እግዚአብሔር ለአብርሃም
ወለዘርኡ ከመ ያእምሩ ከመ አኮ በገቢረ ሕገገ ኦሪት
ዘይጸድቁ ዘእንበለ ዳእሙ በአሚን ።
፲፯ በከመ አምነ አብርሃም አበ ኵልነ ዘይቤሎ እግዚአ
ብሔር እሬስየከ አባሆሙ ለብዙኃን አሕዛብ እለ የአ
ምኑ በእግዚአብሔር ዘያነሥኦሙ ለሙታን ወይሬስ
ዮሙ ለእለ ኢሀለዉ ከመ ዘሀለዉ ።
፲፰ ወተአመነ አብርሃም ከመ ይከውን አባሆሙ ለብዙ
ኃን አሕዛብ ከመ አሰፈዎ እግዚአብሔር ወይቤሎ
ከማሁ ይከውን ዘርእከ ።

ክፍል ፲ወ፱ ፡ በእንተ ጽንዓ ሃይማኖቱ ለአብርሃም ።

፲፱ ወተአመነ አብርሃም ወኢናፈቀ እንዘ ይሬኢ ርእሶ
ከመ ልሂቅ ውእቱ ወከመ ነፍስተ በድን ሥጋሁ
እስመ ምእት ክረምቱ ወሳራሂ ከመ ምውት
ውእቱ ማኅፀና ።
፳ ወኢናፈቀ ወኢቀብፀ በዘአሰፈዎ እግዚአብሔር ።
፳፩ ወተአመነ በኵሉ ልቡ ከመ ይክል ገቢረ ሎቱ እግ
ዚአብሔር ወአእኰቶ ።
፳፪ ወእንበይነዝ ጽድቀ ኮኖ ።
፳፫ ወአኮ እንበይነ ባሕቲቱ ዘተጽሕፈ ዝንቱ ።



አብርሃም ምን ጊዜ ከበረ? ተገዝሮ ነው ወይስ ሳይ ፲
ገዘር ? ተገዝሮ አይደለም ሳይገዘር ነው እንጂ ።
ግዝረት የጽድቅ ማኅተም ትሆነው ዘንድ እሷን ምል ፲፩
ክት አድርጎ ሰጠው ፡ ያንጊዜ ሳይገዘር እግዚአብሔር
አብርሃምን በሃይማኖት እንደ አከበረው በርሱ ላይ
ይታወቅ ዘንድ ሳይገዘሩ ለሚያምኑ ሁሉ ፡ አባት ሊሆን
አብርሃም በሃይማኖት እንደከበረ እነሱም በሃይማ
ኖት እንዲከብሩ ያውቁ ዘንድ ። ዘፍ ፲፯ ፲-፲፩ ።
ሉቃ ፲፱ ፲ ። ዮሐ ፰ ፴፫ ።
የግዙራን አባት ይሆን ዘንድ ለግዙራን ለብቻቸው ፲፪
አይደለም ሳይገዘሩ የአባቶቻችን የአብርሃምን ሃይማ
ኖቱን ፍለጋ ለሚከተሉ ጭምር ነው እንጂ ፡ እርሱ
አባታችን አብርሃም ሳይገዘር እንደ አመነ ። ማቴ ፫ ፱ ።

ክፍል ፲፰ ፡ ስለ አብርሃምና ስለ ዘሩ ተስፋ ።

ዘሩ ዓለምን ይወርስ ዘንድ አብርሃም ተስፋ ያገኘ ፲፫
የኦሪትን ሥራ በመሥራት አይደለም ፡ እግዚአብሔር
ስለ ነገረው እሱንም በማመኑ በእውነተኛ ሃይማኖቱ
ይህን አገኘ እንጂ ። ዘፍ ፲፰ ፲፰ ።
የኦሪትን ሕግ የፈጸመ ብቻ ተስፋ የሚያገኝ ዓለም ፲፬
ንም የሚወርስ ቢሆንስ ኖሮ አብርሃምን ሃይማኖቱ
ባልጠቀመው ነበር ። ገላ ፫ ፲፰ ። ገላ ፫ ፳፱ ።
የኦሪትን ሕግ በአፍራሹ ላይ ቅጣትን ያመጣልና ፲፭
ኦሪት ከሌለ ሕግም ከሌለ ዕዳ በደል የለም ።
ስለዚህም እግዚአብሔር ጽድቅን አደረገ፡ እግዚአብ ፲፮
ሔር ለአብርሃምና ለዘሩ የሰጠው ተስፋ የታመነ
ይሆን ዘንድ የሚከብሩ በሃይማኖት እንጂ የኦሪትን
ሕግ በመፈጸም እንዳይደለ ያውቁ ዘንድ ። ገላ ፫ ፲፰ ።
እግዚአብሔር ሙታንን በሚያስነሣባቸው የሌሉትን ፲፯
እንዳሉ በሚያደርጋቸው በእግዚአብሔር ለሚያምኑ
ለብዙዎች አሕዛብ አባት አደርግሃለሁ ያለውን ቃል
የሁላችን አባት አብርሃም እንዳመነ ። ዘፍ ፲፯ ፭ ።
ዘርህ እንዲሁ ይሆናል ብሎ እግዚአብሔር ተስፋ ፲፰
እንደሰጠው የብዙዎች አባት እንደሚሆን አብርሃም
አመነ ። ዘፍ ፲፭ ፭ ።

ክፍል ፲፱ ፡ ስለ አብርሃም ሃይማኖት ፍጹምነት ።

አብርሃም ራሱን እንደአረጀ አካሉም ሙቀት ልም ፲፱
ላሜ እንደተለየው ሳራም ማኅፀኗ እንደ ደረቀ ሲያ
ውቅ አመነ አልተጠራጠረም ። ዘፍ ፲፯ ፲፯ ።
አልተጠራጠረም እግዚአብሔር በአናገረለት ተስ ፳
ፋም ይቀራል አላለም ። ዕብ ፲፩ ፯-፲፩ ።
እግዚአብሔር ሊያደርግለት እንደሚችል በፍጹም ፳፩
ልቡ አምኖ አመሰገነው ። መዝ ፻፲፭ ፫ ። ኢሳ ፶፱ ፩ ።
ስለዚህም ጽድቅ ሆኖ ተቈጠረለት ። ቀኖ ፫ ። ፳፪
ይህ የተጻፈ ስለርሱ ብቻ አይደለም ። ምዕ ፲፭ ፬ ። ፳፫

፳፬ አከኑ በእንቲአነሂ እለ አመነ በዘአንሥኦ ለእግዚእነ
እሙታን ።
፳፭ ዘተሰቅለ በእንተ ኃጢአትነ ወተንሥአ ከመ ያንሥ
አነ ወከመ ያጽድቀነ ።

## ምዕራፍ ፭ ።

### ክፍል ፰ ፡ በእንተ ጽድቀ ሃይማኖት ።

፩ ጽደቁ እንከ በአሚን ወንርከብ ሰላመ በኀበ እግዚአ
ብሔር በእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ።

፪ ዘበእንቲአሁ ተመራሕነ በሃይማኖት ውስተ ዛቲ
ጸጋሁ እንተ ባቲ ቆምነ ወውእቱ ምክሕነ ወበቲ
ንሴፎ ስብሐተ እግዚአብሔር ።

፫ ወአኮ በባሕቲታ ዓዲ ንትሜከሕ በሕማምነሂ እስመ
ነአምር ከመ ሕማም ይፌጽም ትዕግሥተ ላዕሌነ ።

፬ ወትዕግሥትሰ መከራ ወበመከራ ይትረከብ ተስፋ ።
፭ ወተስፋኒ ኢያስተኀፍር እስመ ፍቅረ እግዚአብሔር
መልአ ውስተ ልብነ በመንፈስ ቅዱስ ዘወሀበነ ።

### ክፍል ፰ወ፩ ፡ በእንተ ምጽአተ ክርስቶስ ።

፮ ክርስቶስኒ መጽአ በዕድሜሁ ይሙት በእንተ ኃጢ
አትነ እንዘ ኃጥአን ንሕነ ።
፯ እንበይነ እኩያንሰ እምዕፁብ ጥቀ ኢይትረከብ ዘይ
ትሀበል ይሙት፡ ወእንበይነ ኄራንሰ እንዳዒ እንጋ
ለእመቦ ዘይትረከብ ዘያጠብዕ ይሙት ።
፰ ናሁ ርእዩ መጠነ አፍቀረነ እግዚአብሔር እንዘ ኃጥ
አን ንሕነ ክርስቶስ ሞተ በእንቲአነ ።

፱ እፎ እንከ ፈድፋደ ለእመ ጸደቅነ ያነጽሐነ በደሙ
ወያድኅነነ እመንሱት ዘይመጽእ ።

፲ ወሶበ እንዘ ፀሩ ንሕነ ለእግዚአብሔር ተሠሃለነ
በሞተ ወልዱ እፎ እንከ ይሠሀለነ ፈድፋደ ወእም
ከመ ተዓረቀነ ወተሠሀለነ ያሕይወነ በሕይወተ
ወልዱ ።
፲፩ አኮ በእንተ ዝንቱ ባሕቲቱ ዓዲ ንትሜካሕ በኀበ እግ
ዚአብሔር በእንተ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ዘበ
እንቲአሁ ረከብነ ሣህሎ ።

### ክፍል ፰ወ፪ ፡ በእንተ ኃጢአት ዘበአት ውስተ ዓለም ።

፲፪ ወበእንተዝ በከመ በጌጋየ አሐዱ ብእሲ በአት ኃጢ
አት ውስተ ዓለም በእንተ ይእቲ ኃጢአት መጽአ ሞት
ላዕለ ኵሉ ሰብእ ወተኰለቈት ኃጢአት ላዕለ ኵሉ ።



ጌታችን ከሙታን ለይቶ ባስነሣው ላመንና ስለኛም ፳፬
ነው እንጂ ። ግብ ሐዋ ፪ ፳፬ ።
ስለ ኃጢአታችን የተሰቀለውን ሊያስነሣን ሊያከ ፳፭
ብረን የተነሣውን ። ኢሳ ፶፫ ፬-፭ ። ፩ ቆሮ ፲፭ ፲፯ ።

## ምዕራፍ ፭ ።

### ክፍል ፰ ፡ በሃይማኖት ስለሚገኘው ክብር ።

እንግዲህ በሃይማኖት ከበሩ በእግዚአብሔር ዘን ፩
ድም በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ሰዉነት ዕርቅን
እናግኝ ። ኢሳ ፶፫ ፭ ። ዮሐ ፲፯ ፲፫ ።
ቤዛ ስለሆነ በሃይማኖት ወደ ጸናንበት ወደዚች ወደ ፪
ልጅነት የደረስንበት መመኪያችንም እሱ ነው ፡ በል
ጅነት እግዚአብሔር የሚሰጠንን ክብር ተስፋ እናደ
ርጋለን ። ኤፌ ፫ ፲፪ ።
የምንመካ በልጅነት ብቻ አይደለም በመከራችንም ፫
ደግሞ እንመካለን እንጂ መከራ በኛ ላይ ትዕግሥ
ትን ፍጹም እንደሚያደርገው እናውቃለንና ።
ትዕግሥት ፈተና ነው በፈተናም ተስፋ ይገኛል ። ፬
ተስፋም አያሳፍርም በሰጠን በመንፈስ ቅዱስ የእግ ፭
ዚአብሔር ፍቅር በልቡናችን መልቶአልና ። ፊል ፩
፳ ። ዕብ ፮ ፲፰-፲፱ ።

### ክፍል ፰፩ ፡ ስለ ክርስቶስ መምጣት ።

እኛ ኃጢአተኞች ስንሆን በኃጢአታችን ምክንያት ፮
ይሞት ዘንድ ክርስቶስ በቀጠሮው መጣ ።
ስለ ክፉዎችማ ሊሞት የሚደፍር በጭንቅ እንኳ ፯
ቢሆን የሚሞት አይገኝም ስለ ደጋጉ ሰዎች፡ ሊሞት
የሚደፍር እንዳለ እንጃ ። ዮሐ ፲፭ ፳፫ ።
አሁን እግዚአብሔር እንደወደደን እነሆ እዩ ፡ እኛ ፰
ኃጢአተኞች ስንሆን ክርስቶስ ስለኛ ሞተ ። ዮሐ ፫
፲፮-፳፩ ። ፩ ጴጥ ፫ ፲፰ ።
ጻድቃን ከሆንማ እንዴት በደሙ እጅግ ያነፃን ! ፱
ከሚመጣው መከራስ እንደምን ያድነን ይሆን ? ።
ምዕ ፩ ፲፰ ። ፲፱ ፪-፰ ።
እኛ የእግዚአብሔር ጠላቶቹ ስንሆን በልጁ ሞት ፲
ይቅር ካለን እንደምን እጅግ ይቅር ይለን ይሆን ?
ይቅር ብሎ ከታረቀንም በልጁ ሕይወትነት ያድነ
ናል ። ምዕ ፰ ፯ ። ፪ ቆሮ ፭ ፲፰ ። ዮሐ ፲፬ ፲፱ ።
በዚህ ብቻ አይደለም ስለ ቤዛነቱ ይቅርታውን ባገኘ ፲፩
ንበት በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስም በእግዚአብ
ሔር ዘንድ እንመካለን እንጂ ።

### ክፍል ፰፪ ፡ ወደ ዓለም ስለ ገባችው ኃጢአት ።

ስለዚህም በአንድ ሰው በደል ምክንያት ኃጢአት ፲፪
ወደ ዓለም እንደ ገባች ስለዚችም ኃጢአት በሰው
ሁሉ ላይ ሞት መጣ ፡ ኃጢአት በሁሉ ላይ ተቈ
ጠረች ። ምዕ ፮ ፳፫ ። ዘፍ ፪ ፲፯ ።

፲፫ እስከ አመ መጽአት ኦሪት ሀለወት ኃጢአት ውስተ ዓለም እንዘ ኢትትዐወቅ ምንት ይእቲ እስመ ኢት ትኌለቍ ኃጢአት እስመ ዓዲሁ ኢመጽአ ውእተ አሚረ ሕገገ ኦሪት ።

፲፬ ወበሕቱ ኰነኖሙ ሞት እምአዳም እስከ ሙሴ ለእለሂ አበሱ ወለእለሂ ኢአበሱ በእንተ ይእቲ ኃጢአቱ ለአዳም እስመ ኵሉ በአምሳለ አዳም ተፈጥረ እስመ አዳም አምሳሉ ውእቱ ለዘሀለዎ ይምጻእ ።

፲፭ ወበሕቱ አኮ በአምጣነ ጌጋይነ ዘኮነነ ሐሳበ ጸጋሁ ለእግዚአብሔር ወሰበ በጌጋየ አሐዱ ብእሲ ሞቱ ብዙኃን እፎ እንከ ፈድፋደ በጸጋሁ ለእግዚአብሔር ወበሀብቱ ዘጸገወነ በእንተ አሐዱ ብእሲ ዘውእቱ ኢየሱስ ክርስቶስ ይፈደፍድ ሕይወት ላዕለ ብዙኃን ።

፲፮ ወአኮ በአምጣነ ኃጢአቱ ለአሐዱ ብእሲ ዘኮነነ ሐሳበ ጸጋሁ ለእግዚአብሔር ወሰበ ኵነኔ ኃጢአት እምላዕለ አሐዱ ብእሲ ወጺአ ኵሉ ተቀሥፈ ባቲ እፎ እንከ ፈደፋደ ያነጽሐነ ጸጋሁ እምጌጋይነ ወይሁበነ ሕይወተ ዘለዓለም ።

ክፍል ፳ወ፫ ፡ በእንተ ሕይወት ዘኮነት በክርስቶስ ።

፲፯ ወሰበ ኃጢአቱ ለአሐዱ ብእሲ አንገሠቶ ለሞት ወበ አበሳ አሐዱ ብእሲ ቀነየነ ሞት እፎ እንከ ጸጋሁ ለአሐዱ ብእሲ ኢየሱስ ክርስቶስ ወሀብቱ ያጸድቀነ ወያነግሦ ለነ ለሕይወት ዘለዓለም ።

፲፰ ወበከመ በጌጋየ አሐዱ ብእሲ ተኰነነ ኵሉ ዓለም ከማሁ ካዕበ በጽድቀ አሐዱ ብእሲ ይጸድቅ ኵሉ እጓለ እመሕያው ።

፲፱ ወበከመ በእንተ ዐሊወ አሐዱ ብእሲ ብዙኃን ኮኑ ኃጥአነ ከማሁ ካዕበ በተአዝዞቱ ለአሐዱ ብእሲ ብዙ ኃን ኮኑ ጻድቃነ ።

፳ ኦሪትሰኬ ለምክንያት መጽአት ወተበውአት ከመ ታብዝኃ ለኃጢአት ወኀበ በዝኃት ኃጢአት ሀየ ፈድፈደት ጸጋሁ ለእግዚአብሔር ።

፳፩ ወበከመ አንገሠቶ ኃጢአት ለሞት ከማሁ ታነግሦ ለጽድቅ ጸጋሁ ለእግዚአብሔር ውስተ ሕይወት ዘለ ዓለም በእንተ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ።

ምዕራፍ ፮ ።

ክፍል ፳ወ፬ ፡ በእንተ ጥምቀትን ።

፩ ምንተ እንከ ንብል ንግበርኑ ኃጢአተ ከመ ይፈድ ፍድ ጸጋሁ ለእግዚአብሔር ፡ ሐሰ ።

ኦሪት እስከመጣች ድረስ ኃጢአት ምን እንደሆ ፲፫
ነች ሳትታወቅ በዓለም ውስጥ ነበረች ፡ ኃጢአት ምን
እንደሆነች አትቈጠርም ነበርና ያንጊዜ የኦሪት ሕግ
ገና አልመጣም ነበርና ። ምዕ ፬ ፲፭ ። ፩ ዮሐ ፫ ፬ ።
በዚች በአዳም ኃጢአት ምክንያት ከአዳም እስከ ሙሴ ፲፬
የበደሉትንም ያልበደሉትንም ሞት ገዛቸው ፡ ሁሉ
በአዳም መልክ ተፈጥሮአልና አዳም ይመጣ ዘንድ
ላለው አምሳሉ ነውና ። ፩ ቆሮ ፲፭ ፳፩-፳፪ ።
ነገር ግን የእግዚአብሔር ጸጋው በበደላችን መጠን ፲፭
የሆነብን አይደለም በአንድ ሰው በደል ብዙዎቹ
ከሞቱ በእግዚአብሔር ጸጋ በአንዱ ሰው በኢየሱስ
ክርስቶስ ቤዛነት በሰጠን ሀብቱ በብዙዎች ላይ እን
ዴት ሕይወት ይበዛ ይሆን ! ። ኢሳ ፶፫ ፲፩ ። ፩ ቆሮ
፲፭ ፳፪ ። ዮሐ ፩ ፲፮-፲፯ ። ዕብ ፱ ፳፰ ።
የእግዚአብሔር የጸጋው ግምገማ በአንዱ ሰው ኀጢ ፲፮
አት ልክ የሆነብን አይደለም ፡ ኃጢአት ያመጣቻት
ፍርድ ካንድ ሰው ወጥታ ሰው ሁሉ ከተቀጣበት ቸር
ነቱማ ከበደላችን ምንኛ አጅግ ያድነን ይሆን ! የዘላ
ለምንስ ሕይወት እንዴት ይሰጠን ይሆን ! ።

ክፍል ፳፫ ፡ በክርስቶስ ስለተገኘችው ሕይወት ።

ያንዱ አዳም ኃጢአት ሞትን ካሠለጠነችው በአ ፲፯
ንድ ሰው (አዳም) በደልም ሞት ከገዛን ያንዱ ሰው
የኢየሱስ ክርስቶስ ቸርነትና ስጦታውማ እንዴት
አጅግ ያከብረን ይሆን ! የዘለዓለም ሕይወትንስ ምንኛ
ያበዛልን ይሆን ! ።
በአንድ ሰው (አዳም) በደል ምክንያት ዓለም ሁሉ ፲፰
እንደ ተፈረደበት እንዲሁ ደግሞ በአንዱ ሰው በኢ
የሱስ ክርስቶስ ቸርነት ሰው ሁሉ ይጸድቃል ። ፩ ቆሮ
፲፭ ፳፪ ። ዮሐ ፲፪ ፴፪ ።
በአንድ ሰው አለመታዘዝ ብዙዎች ኃጢአተኞች ፲፱
እንደሆኑ እንዲሁ ደግሞ በአንዱ ሰው በኢየሱስ
ክርስቶስ መታዘዝ ብዙዎች ጻድቃን ሆኑ ። ኢሳ ፶፫
፲፩ ። ፊል ፪ ፰ ።
ኦሪትስ ለምክንያት መጣች ፡ ኃጢአትንም ታበዛት ፳
ዘንድ ተላለፈች ኃጢአት ከበዛችበት ከዚያች የእግ
ዚአብሔር ጸጋ በዛች ። ገላ ፫ ፲፱ ። ሉቃ ፯ ፵፯ ።
፩ ጢሞ ፩ ፲፬ ።
ኃጢአት ሞትን እንደአሠለጠነችው እንዲሁ በጌታ ፳፩
ችን በኢየሱስ ክርስቶስ ቤዛነት የእግዚአብሔር ቸር
ነት ጽድቅን ለዘለዓለም ሕይወት ታሠለጥነዋለች ።
ቍ ፲፯ ። ምዕ ፮ ፳፫ ።

ምዕራፍ ፮ ።

ክፍል ፳፬ ፡ ስለ ተጠመቁ ።

እንግዲህ ምን እንላለን ? የእግዚአብሔር ጸጋ እንዲ ፩
በዛ ኃጢአት እንሥራ ? ፡ አንልም ። ምዕ ፫ ፭ - ፰ ።

፪ አኮኑ ወዳእነ ሞትነ እምኃጢአትነ እፎ እንከ ንክል
ሐይወ ባቲ ።
፫ ወዘንተ ባሕቱ አእምሩ ኵልክሙ ከመ እለ ተጠመ
ቅነ በእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ውስተ ሞቱ ተጠ
መቅነ ።
፬ ወተቀበርነ ምስሌሁ ውስተ ጥምቀት በሞቱ ከመ
በከመ ውእቱ ክርስቶስ ተንሥአ እሙታን በስብሐተ
አቡሁ ከማሁ ንሕነኒ ናንሶሱ ውስተ ሐዳስ ሕይወት ።

፭ ወእመሰኬ ተመሰልናሁ በሞቱ ንትሜሰሎ በሕይ
ወቱሂ ።
፮ ወዘንተ ባሕቱ አእምሩ ከመ ብሉይ ብእሲነ ውእቱ
ዘተሰቅለ ምስሌሁ ከመ ይሥዓሮ ለነፍስተ ኃጢአት
ወኢይገብእ ዳግመ ይትቀነይ ለኃጢአት ።

፯ እስመ ዘሞተሰ ድኅነ እምገቢረ ኃጢአት ።

<u>ክፍል ፳ወ፫፡ በእንተ እለ ይትሜሰልዎ ለክርስቶስ ።</u>

፰ ወእምከመሰ ሞትነ ምስሌሁ ለክርስቶስ ንትአመን
ከመሂ ነሐዩ ምስሌሁ ።
፱ ተአምሩ ከመ ተንሥአ ክርስቶስ እምውታን ወኢይ
መውት እንከ ዳግመ ወኢይረክቦ እንከ ሞት ።

፲ ወዘኒ ሞተ ምዕረ ሞተ ወበሞቱ ሠዐራ ለኃጢአት ፥
ወዘኒ ሐይወ ለእግዚአብሔር ሐይወ ።

፲፩ ወከማሁ አንትሙኒ ረስዩ ርእሰክሙ ምውታነ ለኃ
ጢአት ወሕያዋነ ኵሉ ለፈቃደ እግዚአብሔር በእ
ንተ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ።

፲፪ ወኢታንግሥዋ ለኃጢአት ላዕለ ዝንቱ ሥጋክሙ
ወነፍስትክሙ መዋቲ ወኢትበልዎ አሆ ለፍትወቱ ።

፲፫ ወኢትረስይዎ ለነፍስትክሙ ንዋየ ሐቅል ለዐመፃ
ወለኃጢአት አላ ረስዩ ርእሰክሙ ለእግዚአብሔር
ከመ ዘተንሥአ እምውታን ወለነፍስትክሙ ለእግዚ
አብሔር ንዋየ ሐቅል ለጽድቅ ።
፲፬ ወኃጢአትሰ ኢትኴንነክሙ እንከ እስመ ወፃእክሙ
እምገቢረ ሕገገ ኦሪት ወገባእክሙ ውስተ ጸጋ እግዚ
አብሔር ።

<u>ክፍል ፳ወ፬ ፡ በእንተ ምሥጢረ ተአዝዞ ።</u>

፲፭ ምንተ እንከ ንብል ንግበርኑ ኃጢአተ እስመ ወፃእነ
እምገቢረ ሕገገ ኦሪት ወገባእነ ውስተ ጸጋ እግዚአ
አብሔር ፡ ሐሰ ።

፲፮ ወኢተአምሩኑ ከመ ለዘተአዘዝክሙ ወለዘሂ አሆ

ከኃጢአታችንማ ፈጽሞ ተለይተን የለም ! እንዴት ፪
ዳግመኛ በእሷ ጸንተን እንኖራለን ! ። ገላ ፮ ፲፬ ።
በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ የተጠመቅን ሁላችን ፫
በሞቱ እንደተጠመቅን ሁላችሁ ይህን ብቻ ዕወቁ ።
ገላ ፫ ፳፫ ። ቈላ ፪ ፲፪ ።
በሞቱም ከርሱ ጋር ወደ ጥምቀት ገባን እሱ ክር ፬
ስቶስ በአባቱ ጌትነት ከሙታን እንደ ተነሣ እንዲሁ
እኛም በአዲሱ ሕይወት እንኖራለን ። ፩ ቆሮ ፲፭
፳፱ ። ፩ ጴጥ ፫ ፳፩ ። ፪ ቆሮ ፭ ፲፯ ።
በሞቱም ከመሰልነው በሕይወቱም እንመስለዋለን ። ፭
ፊል ፫ ፲-፲፩ ። ፪ ጢሞ ፪ ፲፩ ።
ነገር ግን የኃጢአትን ኃይል ይሽር ዘንድ ከሱ ጋር ፮
የተሰቀለው አሮጌው ሰውነታችን እንደሆነ ይህን
ዕወቁ ለኃጢአትም ይገዛ ዘንድ ዳግመኛ አይመለ
ስም ። ገላ ፭ ፳፬ ። ቈላ ፪ ፲፩ ።
የሞተስ ኃጢአትን ከመሥራት ዳነ ። ገላ ፪ ፲፱ ። ፯

<u>ክፍል ፳፭ ፡ ክርስቶስን ስለሚመስሉት ሰዎች ።</u>

ከክርስቶስ ጋር ከሞትን ከእሱም ጋር እንድንነሣ እና ፰
ምናለን ። ፪ ቆሮ ፭ ፲፩ ። ፪ ጢሞ ፪ ፲፩ ።
ክርስቶስ ከሙታን እንደተነሣ እንግዲህ ወዲህ ዳግ ፱
መኛ እንደማይሞት ሞትም እንደማያገኘው ታውቃ
ላችሁ ። ራእ ዮሐ ፩ ፲፰ ።
የሞተ አንድ ጊዜ ሞተ በሞቱም ኃጢአትን ሽራት ፲
የተነሣም ለእግዚአብሔር ተነሣ ። ኢሳ ፶፫ ፲ ። ዕብ
፱ ፳፯-፳፰ ።
እንዲሁ እናንተም ራሳችሁን ለኃጢአት የሞታችሁ ፲፩
አድርጉ በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስም የእግዚአ
ብሔርን ፈቃድ ለማድረግ ሕያዋን ሁኑ ። ፪ ቆሮ ፭
፲፭ ። ፩ ጴጥ ፪ ፳፬ ።
በዚህ በሚሞት ሥጋችሁና ሰውነታችሁ ኃጢአትን አታ ፲፪
ሠልጥኗት ፥ እሱ ለሥጋዊ ፈቃዱም እሺ በጂ አትበ
ሉት ። ዘፍ ፬ ፯ ። መዝ ፻፲፱ ፻፴፫ ።
ሰውነታችሁን ለዓመፅ ለኃጢአት መሣሪያ አታድር ፲፫
ጉት ፥ ከሙታን ተለይቶ እንደተነሣው ራሳችሁን ለእ
ግዚአብሔር አድርጉ እንጂ ፥ ሰውነታችሁንም ለእግ
ዚአብሔር የጽድቅ መሣሪያ አድርጉ ። ም ፲፪ ፩-፲፰ ፥
እንዲህ ከሆነ ኃጢአት አትሠለጥንባችሁም የኦሪትን ፲፬
ሕግ ከመሥራት ወጥታችሁ ወደ እግዚአብሔር ጸጋ
(ወንጌል) ተመልሳችኋልና ። ምዕ ፭ ፳ ። ፩ ዮሐ ፫ ፮ ።

<u>ክፍል ፳፮ ፡ ስለ መታዘዝ ምሥጢር ።</u>

እንግዲህ ምን እንላለን ? የኦሪትን ሕግ ከመፈጸም ፲፭
ወጥተን ወደ እግዚአብሔር ጸጋ (ወንጌል) ገብተና
ልና ኃጢአት እንሥራ እንላለን ? አንልም ። ምዕ ፭
፲፮-፳፩ ። ዮሐ ፩ ፲፮ ።
ለታዘዛችሁለት እሺ በጂ ለምትሉት እናንተ አገልጋ ፲፮

ትቤሉ አግብርቲሁ አንትሙ ወውስተ ዘኀበርክሙ
ሎቱ አቅነይክሙ ርእሰክሙ ፡ እመሂ ለኃጢአት አሆ
ትብልዋ ወኀበርክሙ ተአብሉ አግብርቲሁ አንትሙ
ትከውኑ ለሞት ፡ ወእመሂ ለጽድቅ አሆ ትብልዋ
ወኀበርክሙ ውስተ ሠናይ አግብርተ እግዚአብሔር
አንትሙ ።
፲፯ እኩት እግዚአብሔር እንዘ አግብርተ ኃጢአት አን
ትሙ ተአዘዝክሙ በኵሉ ልብክሙ ለዘተውህበ
ለክሙ አርአያሁ ለዘትትሚሀሩ ።
፲፰ ወይእዜሰ ተግዕዝክሙ እምኃጢአት ወተቀነይክሙ
ለጽድቅ ።
፲፱ ሕገ ዘሰብእ እብለክሙ እስመ ድኩም ቱስሕተ ነፍስ
ክሙ ዐቀ በከመ ቀዲሙ አቅነይክሙ ርእሰክሙ
ለኃጢአት ወለርኵስ ወለጣዖት ከማሁ ይእዜኒ አቀ
ንዩ ነፍስተክሙ ለጽድቅ ወለቅድሳት ።
፳ እስመ አመ ተቀነይክሙ ለኃጢአት ግዑዛነ ክንክሙ
እምጽድቅ ።
፳፩ ወበውእቱ ፍሬክሙ ዘአሚሁ ናሁ ይእዜ ትትኃፈሩ
በቱ እስመ ድኅሬሁ ሎቱ ሞት ።

፳፪ ወይእዜሰ ተግዕዝክሙ እምኃጢአት ወአቅነይክሙ
ርእሰክሙ ለጽድቅ ፡ ወፈረይክሙ ለቅድሳት ወማኅ
ለቅቱሰ ሕይወት ዘለዓለም ።
፳፫ እስመ ተግባራሰ ለኃጢአት ወረበኀ ዚአሃ ሞት ፡
ወለጸጋ እግዚአብሔርሰ ሕይወት ዘለዓለም በእግዚ
እነ ኢየሱስ ክርስቶስ ።

ምዕራፍ ፯ ።

<u>ክፍል ፳ወ፯ ፤ በእንተ ኵነኔ ኦሪት ።</u>

፩ ኢተአምሩኑ አኃዊነ ሕገ ንነግረክሙ ትለብዉ እስመ
ሕገ ኦሪት ይቀንዮ ለሰብእ እምጣነ ሕያው ውእቱ ።

፪ ከመ ብእሲት እምከመ ባቲ ምት አምጣነ ሕያው
ሀሎ ብእሲሃ እስርት ይእቲ በሕግ ወእምከመሰ ሞተ
ምታ ተሥዕረት እምሕገ ብእሲሃ ።
፫ ወእመሰ እንዘ ሕያው ብእሲሃ ቀርበት ካልአ ብእሴ
ዝሙተ ይከውና ፡ ወለእመሰ ሞተ ምታ ተስዕረት
እምሕግ ወኢትከውን ዘማዊተ ለእመ ከነት ለካልእ
ብእሲ ።
፬ ወይእዜኒ አኃዊነ ሞትክሙ እምኦሪት በእንተ ሥጋሁ
ለክርስቶስ ከመ ትኩኑ ለዳግም ዘተንሥአ እምው
ታን ከመ ትፍረዩ ለእግዚአብሔር ፍሬ ጽድቅ ።

፭ ወእመሰ በሕገ ሰብእ ንገብር ጸንሀ ላዕሌነ መቅሠፍት
በስኢነ ሕገገ ኦሪት ወፈረይነ ለሞት ።

ዮች እንደሆናችሁ አታውቁምን ? ለተባበራችሁለ
ትስ ራሳችሁን እንደ አስገዛችሁ አታውቁምን ? ኃጢ
አትን እሺ በጀ ብትሏት ተባብራችሁም ብትበድሉ
እናንት ለሞት ተገዥዎች ትሆናላችሁ ። ጽድቅን
እሺ በጀ ብትሏት ለበጎ ሥራ ብትተባበሩ የእግዚአ
ብሔር አገልጋዮች ናችሁ ። ዮሐ ፰ ፴፬-፴፭ ።
እግዚአብሔር የተመሰገነ ይሁን ፡ እናንተ የኃጢአት ፲፯
ተገዥዎች ስትሆኑ ለምትማሩለት አብነትነቱ ለተሰ
ጣችሁት እናንት በፍጹም ልቡናችሁ ታዘዛችሁ ።
አሁንም ከኃጢአት ነፃ ሆናችሁ ለጽድቅ ተገዛችሁ ። ፲፰
ዮሐ ፰ ፴፪ ። ገላ ፭ ፩ ። ፩ ጴጥ ፪ ፲፮ ።
የሰውነታችሁ ተፈጥሮ ደካማ ነውና ሰው ሰውኛውን ፲፱
እነግራችኋለሁ ዕወቁ ቀድሞ ዘመን ራሳችሁን ለኃ
ጢአት ለዝሙት ለጣዖት እንደ አስገዛችሁ ፡ አሁንም
እንዲሁ ሰውነታችሁን ለጽድቅ ለንጽሕና አስገዙ ።
ለኃጢአት ትገዙ በነበረ ጊዜ ከጽድቅ ወጥታችሁ ፳
ነበርና ። ዮሐ ፰ ፴፬ ።
ያን ጊዜ ትሠሩ በነበረው ሥራ በዚያ ዛሬ ታፍሩበ ፳፩
ታላችሁ ተከታዩ ሞት ነውና ። ሕዝ ፲፮ ፳፩-፳፪ ።
ምዕ ፰ ፮ ።
ዛሬ ግን ከኃጢአት ተለይታችኋል ራሳችሁንም ለጽ ፳፪
ድቅ አስገዝታችኋል ቅድስናን ገንዘብ አድርጋችኋል
ፍጻሜው ግን የዘለዓለም ሕይወት ነው ። ፩ ጴጥ ፩ ፱ ።
የኃጢአት ሥራዋ ትርፍዋ ሞት ነውና ፡ የእግዚአብ ፳፫
ሔር ጸጋ ግን በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ሰጭነት
የዘለዓለም ሕይወት ነው ። ዘፍ ፪ ፲፯ ። ምዕ ፭ ፲፪ ።
ያዕ ፩ ፲፭ ። ራእ ዮሐ ፳፩ ፰ ።

ምዕራፍ ፯ ።

<u>ክፍል ፳፯ ስለ ኦሪት ፍርድ ።</u>

ወንድሞቻችን ! ታስተውሉ ዘንድ እንድንነግራችሁ ፩
አታውቁምን ? የኦሪት ሕግ በሕይወት ዘመኑ ሰውን
ይገዛው ነበርና ።
ሴት ባል ያላት እንደሆነ ባሏ በሕይወት እስካለ ድረስ ፪
በሕግ የታሠረች እንደሆነች ባሏ የሞተ እንደሆነ ግን
በሚስትነት ታሥራበት ከኖረችው ሕግ እንድትፈታ ።
ባሏ በሕይወት እያለ ከሌላ ሰው ብትደርስ ዝሙት ፫
ይሆንባታል ፡ ባሏ የሞተ እንሆነ ግን ከሕግ ተፈታለች
ሌላ ሰው ብታገባ አመንዝራ አትባልም ። ማቴ ፭ ፴፪ ።

ወንድሞቻችን ! አሁንም የክርስቶስ አካል ስለሆናችሁ ፬
ከኦሪት ተለያችሁ ከሙታን ተለይቶ ለተነሣው ለዳግ
ማዊ (አዳም) ማደሪያ ትሆኑ ዘንድ ለእግዚአብሔር
የጽድቅ ፍሬን ታቀርቡ ዘንድ ። ኤፌ ፯ ፴፩-፴፪ ።
ሰው ሠራሽ ሕግን እንሠራ በነበረበት ጊዜ የኦሪትን ፭
ሕግ ባለመፈጸማችን ቅጣቱ ጸንቶብን ነበር ለሞት
የሚያደርስም ፍሬ አፍርተን ነበር ። ቆላ ፯ ፳፭ ።

፮ ወይእዜሰ ተሰዐርነ እምኦሪት ወኀደግነ ዘቀዲሙ
ትምህርተነ ከመ ንትቀነይ በሕገ መንፈስ ወአኮ በብ
ሉይ መጽሐፍ ።

ክፍል ፳ወ፫ ፥ በእንተ መንኖተ ኦሪት ።

፯ ምንተ እንከ ንብል ኃጢአትኑ ይእቲ ኦሪት ሐሰ፤
ወበሕቱ እምኢያእመርክምዋ ለኃጢአት ሶበ ኢመ
ጽአት ኦሪት ወለፍትወትኒ እምኢያእመርክምዋ
ግሙራ ሶበ ኢትቤ ኦሪት ኢትፍቱ ።
፰ ወምክንያተ ኮነታ ይእቲ ትእዛዝ ለኃጢአት ወአም
ጽአት ላዕሌየ ኵሎ ፍትወታተ ወቀዲሙሰ ዘእንበለ
ትምጻእ ኦሪት ምውት ይእቲ ኃጢአት ።

፱ ወአንሂ ሐዮኩ ትካት ዘእንበለ ትምጻእ ኦሪት ወሰበ
መጽአት ትእዛዘ ኦሪት ሐይወት ኃጢአት ወአንሰ
ሞትኩ ።
፲ ወኮነተኒ ቀታሊተ እንታክቲ ትእዛዘ ሕይወት ።

፲፩ እስመ ኮነታ ምክንያተ ይእቲ ትእዛዝ ለኃጢአት
ወበእንቲአሃ አስሐተተኒ ወቀተለተኒ ።
፲፪ ወይእዜኒ ኦሪትሰ ቅድስት ይእቲ ወትእዛዝኒ ጽድቅ
ውእቱ ፥ ወሠናይ ፥ ወበረከት ።
፲፫ እብል እንከ ቦኑ ሊተ ይከውነኒ ቀታሌ ዝኩ ዘሠናየ
አሐስብ ሐሰ ፥ ዳእሙ ኃጢአት ሶበ ተዐውቀት ከመ
ይእቲ ኃጢአት አብዝኃት ላዕሌየ ሞተ ፥ አኮኑ ከመ
ይትዐወቅ ኃጥእ ወከመ ትትአመር ኃጢአት እምው
እቱ ትእዛዝ መጽአት ኦሪት ከመ ትፍልጥ ሠናየ
እምእኩይ ።

ክፍል ፳ወ፬ ፥ በእንተ ሕገ መንፈስ ።

፲፬ ነአምር ከመ ሕገ ኦሪትሰ ለመንፈስ ወአንሰ በሥጋ
ወደም ሥዩጥ ለኃጢአት ።

፲፭ እስመ ዘኢየአምር እገብር ወዘእፈቅድ ኢይገብር
ኪያሁ ምንተኒ ፥ ዳእሙ ዝኩ ዘእጸልእ ኪያሁ ክመ
እገብሮ ።
፲፮ ወእመሰኬ ዘኢይፈቅድ እገብር ሰማዕቱ አነ ለዝኩ
ሕገገ ኦሪት ከመ ለሠናይ መጽአ ።
፲፯ ወይእዜሰኬ ኢኮንኩ አነ ገባሪሁ ለውእቱ አላ ኃጢ
አት እንተ ኃደረት ላዕሌየ ይእቲ ትገብሮ ።

፲፰ ወአአምር ከመ ኢየኀድር ላዕሌየ ሠናይ በእንተ
ሥጋየ ፥ ፈቂደ ገቢረ ሠናይሰ ሀሎ ኀቤየ ፥ ወምግባረ
ሠናይሰ አልብየ ።

፲፱ ወአኮሰ ዘእገብር ኪያሁ ዘእፈቅድ ዳእሙ ዝኰ እኩየ
ዘእጸልእ ኪያሁ እገብር ።

አሁንማ ከኦሪት ተለይተናል የቀደመ ትምህርታች ፮
ንን ትተናል በብሉይ መጽሐፍ ያይደለ በመንፈሳዊ
ሕግ እንገዛ ዘንድ ። ፫ ፩-፲፪ ። ፮ ፪-፬ ።

ክፍል ፳፫ ፥ ኦሪትን ስለ መናቅ ።

እንግዲህ ምን እንላለን ? ኦሪት ኃጢአት ናት እንላ ፯
ለን ? አላልንም ፥ ነገር ግን ኦሪት ባትሠራ ኃጢአትን
ባላወቃችኋትም ነበር ፥ ኦሪት አትመኙ ባትል ኖሮም
ምኞትን ፈጽሞ ባላወቃችኋትም ነበር ። ዘፀ ፳ ፲፯ ።
አትመኝ የምትለው ትእዛዝ ለኃጢአት ምክንያት ፰
ሆነቻት ፡ ምኞትን ሁሉ ሰብሰባ አመጣችብኝ ቀድ
ሞማ ኦሪት ሳትሠራ ኃጢአት ሙት ነበረች ። ቆላ ፲፩፤
ምዕ ፭ ፲፫ ። ዮሐ ፲፭ ፳፪ ።
እኔም ቀድሞ ኦሪት ሳትሠራ ደኅና ነበርኩ ፥ የኦሪት ፱
ትእዛዝ በመጣች ጊዜ ግን ኃጢአት ዳነች እኔ ግን
ሞትኩ ።
ሕይወት ላገኝበት የተሠራችልኝ ያች ሕግ አጥፊ ፲
ሆነችኝ ። ያዕ ፩ ፲፭። ዘሌዋ ፲፰ ፭።
ይህች ትእዛዝ ለኃጢአት ምክንያት ሆናታለችና ስለ ፲፩
አልፈጸምኳት አሳተችኝ አጠፋችኝ ። ዕብ ፫ ፲፫ ።
አሁንም ኦሪትስ ቅድስት ናት ትእዛዟም እውነት ፲፪
ነው መልካም ነው ፥ በረከት የሚገኝበትም ነው ።
እንግዲህ ያ መልካም ነው ብዬ የማስበው ነገር ፲፫
በውኑ አጥፊ ይሆንብኛል? አይሆንም ፥ ግን ኃጢ
አት እንደሆነች በታወቀች ጊዜ ሞትን አበዛች
ብኝ ከዚያ ትእዛዝ የተነሣ ኃጢአተኛው እንዲታ
ወቅ ኦሪት መልካሙን ከክፉ ልትለይ ተሠርታ
ለችና ። ምዕ ፭ ፳ ።

ክፍል ፳፬ ስለ መንፈሳዊ ሕግ ።

የኦሪት ሕግ ለልቡና አጋዥ እንደሆነ እናውቃለን ፥ ፲፬
እኔ ግን ሥጋ ደም በመሆኔ ምክንያት ለኃጢአት
የተሸጥኩ ነኝ ። ማቴ ፭ ፳፪-፳፰ ። ዮሐ ፫ ፮ ።
የማልወደውን እሠራለሁና፤ የምወደውንም ያን ከቶ ፲፭
አላደርገውም ፥ ያንኑ የምጠላውን እሱ ብቻ እሠራ
ለሁ እንጂ ።
የማልወደውንስ የምሠራ ከሆንኩ ያ የኦሪት ሕግ ለመ ፲፮
ልካም እንደ ተሠራ ምስክሩ እኔ ነኝ ። ቆላ ፲፪ ።
እንግዲያስ ያን የምጠላውን የምሠራው እኔ አይደ ፲፯
ለሁም በኔ ላይ ያደረች ኃጢአት እርሷ ትሠራዋለች
እንጂ ።
ስለ ሥጋዬ በእኔ መልካም ነገር እንደማይኖር አው ፲፰
ቃለሁ ፥ መልካም ሥራ ለመሥራት መሻቱማ በኔ
ዘንድ አለ በጎ ምግባር ግን የለኝም ። ዘፍ ፮ ፭ ።
ምዕ ፫ ፳፩ ።
ያን የምወደውን የማደርግ አይደለም ፥ ያንኑ የምጠ ፲፱
ላውን ክፉውን አደርጋለሁ እንጂ ።

ክፍል ፴ ፡ በእንተ ድክም ዓቅመ ሰብእ ።

፳ ወእመሰኬ ዘኢይፈቅድ እገብር ኢኮንኩኬ አነ ዘእ
ገብሮ አላ ኃጢአት እንተ ኀደረትላዕሌየ ይእቲ
ትገብሮ ።
፳፩ ወረከብክዎ ለዝኩ ሕግ ዘፈቀደ ሊተ እግበር ሠናየ
ውእቱ አምጽአ ላዕሌየ እኩየ ።
፳፪ ሐዋዝ ውእቱ ሕገ እግዚአብሔር ዘውስተ ልብየ ።
፳፫ ወበሕቱ እረክብ ካልአ ሕገ ኃጢአት ውስተ አበልየ
ወተፃብኦ ወተቃትሎ ምስለ ዝኩ ሕገ እግዚአብሔር
ዘውስተ ልብየ ወኃየሎ ዝኩ ሕገ ኃጢአት ዘውስተ
አበልየ ወፄወወኒ መንገሌሁ ።
፳፬ ትሑት ብእሲ አነ መኑ እምአድኀነኒ እምዝንቱ ነፍ
ስትየ መዋቲ ።
፳፭ እኩት እግዚአብሔር በእንተ እግዚእነ ኢየሱስ ክር
ስቶስ እንሰ ሎቱ እትቀነይ በልብየኒ ወበሕሊናየኒ
ለሕገ እግዚአብሔር ወበነፍስትየኒ ለሕገ ኃጢአት ።

ምዕራፍ ፰ ።

ክፍል ፴ወ፩ ፡ በእንተ ስኢነ ሕገ ኦሪት ።

፩ ወአልቦሙ እንከ ኵነኔ ለእለ የኀድጉ ምግባረ ሥጋ
በኢየሱስ ክርስቶስ ።
፪ እስመ ሕገ መንፈስ ዘሕይወት ዘተውህበ በኢየሱስ
ክርስቶስ ውእቱ አግዐዘነ እምሕገ ኃጢአት ወሞት ።
፫ ወሰበ ተስእኖ ለሕገ ኦሪት ላዕለ ሞት በእንተ ድከመ
ሥጋ ፈነወ እግዚአብሔር ወልዶ በአምሳለ ነፍስተ
ኃጢአት ወኮነና ለይእቲ ኀጢአት በነፍስቱ ።
፬ ወከመ ያጽድቀነ ኪያነ ወከመ ይረሲ ለነ ከመ ዘፈ
ጸመ ገቢሮቶ ለሕገ ኦሪት ለእለ በሕገ መንፈስ የሐ
ውሩ ወአኮ ለእለ በሕገ ነፍስቶሙ ይገብሩ ።
፭ እስመ ኵሎሙ እለ ለግዕዘ ነፍስቶሙ ይገብሩ ዘዝ
ንቱ ዓለም ይሔልዩ፡ ወእለሰ ዘመንፈስ ይሔልዩ
ዘመንፈስ ።

ክፍል ፴ወ፪፡ በእንተ ሕሊና ሥጋ ወሕሊና መንፈስ ።

፮ ወሕሊናሁሰ ለነፍስትነ ሞተ ያመጽእ ላዕሌነ፡ ወሕሊ
ናሁሰ ለመንፈስ ሰላመ ወሕይወተ ይሁበነ።
፯ እስመ ሕሊናሁ ለነፍስትነ ፀሩ ለእግዚአብሔር
ውእቱ፡ እስመ ኢይገርር ለሕገ እግዚአብሔር ወኢሂ
ይክሎ ።
፰ እስመ ኵሎሙ እለ ለግዕዘ ነፍስቶሙ ይገብሩ ለእግ
ዚአብሔር አድልዎ ኢይክሉ ።



ክፍል ፴ ፡ ስለ ሰው ዓቅም ደካማነት ።

የማልወደውን ከሠራሁ የምሠራው እኔ አይደለ ፳
ሁም ፡ በኔ ላይ ያደረች ኃጢአት ናት እንጂ ።
መልካም ሥራ እንድሠራ የፈቀደልኝን ያንን ሕግ ፳፩
እርሱ ክፉ ነገር አምጥቶብኝ አገኘሁት ። ዘፍ ፬ ፯ ።
መዝ ፶፩ ፪ ።
በልቡናየ ውስጥ ያለ የእግዚአብሔር ሕግ ያማረ ፳፪
ነው ። ምዕ ፪ ፲፬-፲፭ ። መዝ ፩ ፪ ።
ግን በሰውነቴ ውስጥ ሌላ የኃጢአት ሕግ አገኛለሁ ፳፫
በልቡናየ ውስጥ ካለው የእግዚአብሔር ሕግ ጋር
ተሰላልፈው ተዋጉ ግን በሰውነቴ ውስጥ ያለ ያ የኃ
ጢአት ሕግ ድል ነሥቶ ወደርሱ ማረከኝ ። ገላ ፭ ፲፯ ።
እኔ ወራዳ ሰው ነኝ ከዚህ ከመዋች በስባሽ ሰውነቴ ፳፬
ማን ባዳነኝ? ። ምዕ ፰ ፲ - ፲፰ ።
ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስን ቤዛ አድርጎ ስለ አዳነኝ ፳፭
እግዚአብሔር ይክበር ይመስገን ፡ እኔ በልቤም በሐ
ሳቤም ለእግዚአብሔር ሕግ እገዛለሁ ፡ በሰውነቴ ግን
ለኃጢአት ሕግ እገዛለሁ ። ፩ ቆሮ ፲፭ ፶፯ ።

ምዕራፍ ፰ ።

ክፍል ፴፩ ፡ የኦሪት ሕግ ሰውን ማዳን ስለ ተሳነው ።

እንግዲህ በኢየሱስ ክርስቶስ ሥጋዊ ሥራን በሚ ፩
ተው ፍርድ የለባቸውም ። ገላ ፭ ፲፯-፳፭ ።
በኢየሱስ ክርስቶስ የተሰጠን ሕይወት የሚገኝበት ፪
የመንፈሳዊ ሕግ እሱ ከሞትና ከኃጢአት ሕግ ነፃ
አውጥቶናልና ። ምዕ ፫ ፳፯ ።
ስለ ሥጋ ደካማነት የኦሪት ሕግ ከሞት ማዳን በተሳ ፫
ነው ጊዜ እግዚአብሔር ኃጢአት በሚስማማው
አካል መልክ ልጁን ላከ ። ግብ ሐዋ ፲፫ ፴፰ ።
እኛን ያከብረን ዘንድ የኦሪትን ሕግም እንደፈጸመ ፬
ሰው ያደርገን ዘንድ ይህም በመንፈሳዊ ሕግ ጸንተው
ለሚኖሩ ነው እንጂ ፡ በሥጋዊ ሥራ ፈቃዳቸው ለሚ
ሠሩ አይደለም ።
በሥጋቸው ፈቃድ የሚሠሩ ሁሉ የዚህን ዓለም ያስ ፭
ባሉ ፡ የእግዚአብሔር የሆኑ ግን የእግዚአብሔርን ያስ
ባሉ ። ዮሐ ፬ ፡ ፳፬ ፤ ቆላ ፲፬ ።

ክፍል ፴፪ ፡ ስለ ሥጋዊ ሐሳብና ስለ መንፈሳዊ ሐሳብ ።

የሥጋችን ሐሳብ ሞትን ያመጣብናል ፡ ስለ እግዚአብ ፮
ሔር ማሰብ ግን ሰላምንና ሕይወትን ያሰጠናል ።
የሥጋችን ሐሳብ የእግዚአብሔር ጠላት ስለሆነ ፡ ለእ ፯
ግዚአብሔር ሕግ አይገዛምና መፈጸምም አይችለው
ምና ። ያዕ ፬ ፡ ፬ ።
ለሥጋዊ ፈቃዳቸው የሚሠሩ ሁሉ እግዚአብሔርን ፰
ደስ ማሰኘት አይችሉምና ።

፱ ወአንትሙሰ አኮ ለግዕዘ ነፍስክሙ ዘትገብሩ ዘእ
ንበለ ለሕገ መንፈስ እስመ መንፈሰ እግዚአብሔር
ኀዱር ላዕሌክሙ ወዘሰ አልቦ መንፈሰ ክርስቶስ ላዕ
ሌሁ ውእቱ ዘኢኮነ ዚአሁ ።
፲ ወእመሰ ክርስቶስ ምስሌክሙ ምውት ረስዩ ነፍስተ
ክሙ ለምግባረ ኃጢአት ፡ ወሕያወ ረስዩ መንፈሰ
ክሙ ለምግባረ ጽድቅ ።
፲፩ ወእመሰ መንፈሱ ለዘአንሥኦ ለኢየሱስ እምውታን
ኀዱር ላዕሌክሙ ውእቱ ዘአንሥኦ እምውታን ለኢ
የሱስ ያሐይዋ ለነፍስክሙኒ በውእቱ መንፈሱ ዘየ
ኀድር ላዕሌክሙ ።

ክፍል ፴ወ፫ ፡ በእንተ ዘኢይደሉ አዝልፎ ምግባረ ሥጋ ።

፲፪ ወይእዜኒ አኀዊነ ኢርቱዕ ንግበር ለግዕዘ ነፍስትነ
እንዘ ሀሎነ በነፍስትነ ።
፲፫ እስመ ኵሎሙ እለ ለግዕዘ ነፍስቶሙ ይገብሩ ምዉ
ታን በላዕሉ እሙንቱ ወእመሰ በምግባረ መንፈስ ቀተ
ልክምዎ ለምግባረ ነፍስትክሙ ተሐይዉ ለዓለም ።
፲፬ እስመ ኵሎሙ እለ ይገብሩ በመንፈሰ እግዚአብሔር
ውሉደ እግዚአብሔር እሙንቱ ።
፲፭ ወዘአኮ ካዕበ ነሣእክሙ መንፈሰ ቅኔ በዘትፈርሁ
አላ ነሣእክሙ መንፈሰ ዘይሁበክሙ ትርሢተ ወልድ
ወትጸርሑ ሎቱ ወትብልዎ አባ ወአቡየ ።
፲፮ ውእቱ መንፈስ ቅዱስ ሰማዕቱ ለመንፈስነ ከመ
ውሉደ እግዚአብሔር ንሕነ ።
፲፯ ወእምከመሰ ውሉደ እግዚአብሔር ንሕነ ወራስያኒሁ
ንሕነ ፡ ወእምከመሂ ወራስያነ እግዚአብሔር ንሕነ
መዋርስቲሁ ለክርስቶስ ንሕነ ፡ ወእምከመሰ ዐረይነ
ሕማመ ንኄሬ ክብረ ምስሌሁ ።

ክፍል ፴ወ፬ ፡ በእንተ መንግሥተ ሰማያት ።

፲፰ ወባሕቱ ሐልይዋ ለዛቲኒ ከመ ኢከነት መጠነ ሢጣ
ለእንታክቲ ክብር ወስብሐት እንተ ለዓለም ሕማሙ
ለዝ ዓለም ።
፲፱ እስመ ተስፋሁ ለዓለም ምጽአቶ ለወልደ እግዚአብ
ሔር ይጸንሕ ።
፳ እስመ ለከንቱ ተቀንየ ዓለም በኢያእምሮ ።
፳፩ ወባሕቱ ቦቱ ተስፋ ከመ ይፃእ እምዘቀነዮ ወይግባእ
ውስተ ስብሐተ ግዕዛኖሙ ለደቂቀ እግዚአብሔር ።
፳፪ ነአምር ከመ ኵሉ ዓለም ሕሙም ወትኩዝ እስከ
ይእዜ ።
፳፫ ወአኮ ዓለም ባሕቲቱ ዓዲ ንሕነሂ ንቴክዝ እለ ነሣእነ



እናንተ ግን ለሥጋችሁ ፈቃድ የምትሠሩ አይደለም ፱
ለመንፈሳዊ ሕግ እንጂ ፡ የእግዚአብሔር መንፈስ በእ
ናንተ አድሮ ይኖራልና የክርስቶስ መንፈስ ያላደረ
በት ግን ወገኑ ያይደለ እሱ ነው ። ፩ ቆሮ ፫ ፡ ፲፯ ።
ክርስቶስ ከናንተ ጋር ከሆነ ግን ራሳችሁን ከኃጢ ፲
አት ሥራ ለዩ ፡ ልቡናችሁንም ለጽድቅ ሥራ ሕያው
አድርጉ ።
ኢየሱስን ከሙታን ለይቶ ያስነሣው የእግዚአብሔር ፲፩
መንፈስ ከደረባችሁ ኢየሱስን ከሙታን ያስነሣው
እርሱ ሰውነታችሁን አድሮባችሁ ባለ በመንፈሱ
ያስነሣታል ።

ክፍል ፴፫ ፡ ሥጋዊ ሥራ ማዘውተር የማይገባ ስለ መሆኑ ።

ወንድሞቻችን አሁንም በሥጋችን ሳለን የሥጋችንን ፲፪
ፈቃድ ልንሠራ አይገባም ። ምዕ ፯ ፡ ፯ - ፲፰ ።
ሥጋዊ ፈቃዳቸውን የሚሠሩ ሁሉ እነርሱ በላይ ፲፫
ኛው ዓለም የሞቱ ናቸው ፡ ግን በመንፈሳዊ ሥራ
የሥጋችሁን ፈቃድ ድል ከነሣችሁት ለዘለዓለም
በሕይወት ትኖራላችሁ ። ገላ ፮ ፡ ፰ ። ኤፌ ፬ ፡ ፳፪ ።
የእግዚአብሔር መንፈስ የሚወደውን ሥራ የሚሠሩ ፲፬
ሁሉ የእግዚአብሔር ልጆች ናቸው ።
ዳግመኛም በምትፈሩ ገንዘብ የመገዛትን ሀብት የተ ፲፭
ቀበላችሁ አይደለም ፡ ወልድን መምሰል የሚሰጣ
ችሁ መንፈስን ተቀበላችሁ እንጂ ፡ ድምፃችሁ ከፍ
አድርጋችሁ አባ አባቴ ብላችሁ ትጠሩታላችሁ ።
የእግዚአብሔር ልጆቹ እንደሆነ የመንፈሳችን ምስ ፲፮
ክሩ እርሱ መንፈስ ቅዱስ ነው ። ፪ ቆሮ ፩ ፡ ፳፪ ።
እኛ የእግዚአብሔር ልጆች ከሆነ ወራሾቹ ነን ፡ የእ ፲፯
ግዚአብሔር ወራሾች ከሆነም የክርስቶስ ተወራራ
ሾቹ ነን ፡ በመከራም ከመሰልነው በክብር እንመስለ
ዋለን ። ግብ ሐዋ ፲፬ ፡ ፳፪ ።

ክፍል ፴፬ ፡ ስለ መንግሥተ ሰማያት ።

ነገር ግን የዚህ ዓለም መከራ ዘለዓለም የሚኖር ለዚ ፲፰
ያች ክብር ጌትነት ለተገኘበት መጠኗ ክብር ጌትነት
እንዳይደለች ይህቺንም አስቧት ። ፪ ቆሮ ፬ ፡ ፲፯ ።
፩ ጴጥ ፩ ፡ ፯ - ፯ ።
የዓለም ተስፋው የእግዚአብሔርን ልጅ መምጣት ፲፱
ደጅ ይጠና ነበርና ። ቈላ ፫ ፡ ፬ ።
ዓለም ባለ ማወቅ ለከንቱ ነገር ስለ ተገዛ ። ዘፍ ፫ ፡ ፳
፲፯ ። ምዕ ፭ ፡ ፳፩ ።
ነገር ግን በባርነት ከሚገዛው እጅ ወጥቶ የእግዚአብ ፳፩
ሔር ልጆች ወደ አገኟት የነፃነት ክብር ይገባ ዘንድ
ተስፋ አለው ። ፪ ጴጥ ፫ ፡ ፲፫ ።
“እስከሁን ዓለም ሁሉ የሚያዝን የሚተክዝ እንደሆነ ፳፪
እናውቃለን„ ። ኤር ፲፪ ፡ ፲፩ ።
ግን የሚተክዘው ዓለም ብቻ አይደለም ፡ የመንፈስ ፳፫

ቀዳሚሁ ለመንፈስ ቅዱስ እስመ ንሴፎ ትርሢተ
ውሉድ ንርከብ መድኃኒተ ነፍስነ እስመ በአሚን
ድኅነ ።

፳፬ እስመ በአሚን ድኅነ ወተሰፈውነ ዘያስተርኢ ኢኮነ
ተስፋ ወዘሰ ይሬኢ እፎ ይሴፎ ወይጸንሕ ።

፳፭ ወእምከመሰ ንሴፎ ዘያስተርኢ ይትዐወቅ ትዕግሥ
ትነ ከመ ተሰፈውናሁ ወቆምነ በእንቲአሁ ።

## ክፍል ፴ወ፭፡ በእንተ ረድኤት ።

፳፮ ወይረድአነ ለነ ድካመነ በመንፈስ ቅዱስ ወምንትኑ
ውእቱ እንከ ጸሎትነ ለእመ ኢነአምር ተስፋነ ወባ
ሕቱ መንፈስ ለሊሁ ይትዋቀሥ ለነ በእንተ ሕማምነ
ወምንዳቤነ ።

፳፯ ወውእቱ የሐትቶ ለልብነ ወየአምር ዘይሔሊ መን
ፈስ ወይትዋቀሥ በኀበ እግዚአብሔር በእንተ ቅዱ
ሳን ።
፳፰ ነአምር ከመ ይረድኦሙ እግዚአብሔር ለእለ ይፈር
ህዎ ውስተ ኵሉ ምግባረ ሠናይ ።

፳፱ እስመ ለእለ ቀደመ ወኀረየ ወአእመሮሙ ኪያሆሙ
ሠርዐ ይኩኑ በአምሳለ ወልዱ ከመ ይኩን ውእቱ
በኵር በላዕለ ብዙኃን አኀው ።

፴ ወለእለ ሠርዐ ኢያሆሙ ጸውዐ፡ ወለእለ ጸውዐ ኪያ
ሆሙ አጽደቀ፡ ወለእለ አጽደቀ ኪያሆሙ አክበረ ።
፴፩ ምንተ እንከ ንብል እንበይነዝ ለእመ እግዚአብሔር
ምስሌነ መኑ ይክለነ ።

፴፪ ወልዶ ጥቀ ኢምሕከ እምኔነ አላ መጠዎ በእንተ
ኵልነ ወምንትኑ ውእቱ እንከ ዘኢይጼግወነ ኵሎ ።
፴፫ ወመኑ ውእቱ እንከ ዘይትዋቀሦሙ ለኅሩያነ እግዚ
አብሔር ።
፴፬ ለእመ ለሊሁ ያጸድቅ መኑ ዘይኴንን ክርስቶስ ሞተ
ወተንሥአ እምውታን ወሀሎ ይነብር በየማነ እግዚአ
ብሔር ወይትዋቀሥ በእንቲአነ ።

## ክፍል ፴ወ፮፡ በእንተ ሰማዕታት ።

፴፭ መኑ ያኀድገነ ፍቅሮ ለክርስቶስ፡ ሕማምኑ፡ ምንዳቤኑ
ተሰዶኑ፡ ረኃብኑ፡ ዕርቃንኑ፡ መጥባሕትኑ፡ ፃዕርኑ ።

፴፮ በከመ ይቤ መጽሐፍ በእንቲአከ ይቀትሉነ ኵሎ
አሚረ ወኮነ ከመ አባግዕ ዘይጠብሑ ።



ቅዱስን ፈለግ የተቀበልነው እኛም እናዝናለን እንጂ
የልጅነትን ክብር ተስፋ እናደርጋለንና በሃይማኖት
ስለዳን የነፍሳችንን ድኅነት እናገኝ ዘንድ ። ፪ ቆሮ
፭ ፡ ፭ ።
የሚታየውን ተስፋ ማድረግ ተስፋ አይደለም ፡ የሚ ፳፬
ያየውን እንዴት ተስፋ አድርጎ ይጠብቃል?። ፪ ቆሮ
፭ ፡ ፯ ። ዕብ ፲፩ ፡ ፩ ።
የማይታየውን ተስፋ ብናደርግ ግን እሱን ተስፋ አድ ፳፭
ርገን በርሱ እንደፀናን መጠን ደጅ ጥናታችን ይታ
ወቃል ።

## ክፍል ፴፭ ፡ ስለ ረድኤት ።

በመንፈስ ቅዱስም ከድካማችን ይረዳናል እንግዲ ፳፮
ያማ ተስፋችንን ካላወቅነ ጸሎታችን ምንድር ነው?
ነገር ግን ስለ መከራችንና ስለ ፀዋትወ መከራችን
እርሱ ራሱ መንፈስ ቅዱስ ይመልስልናል ። ማቴ
፳ ፡ ፳፪ ። ዮሐ ፲፯ ፡ ፯ - ፲፬ ።
እርሱ ልቡናችንን ይመረምረዋል ፡ ልብ ያሰበውን ፳፯
እርሱ መንፈስ ቅዱስ ያውቃል ፡ በእግዚአብሔር ዘን
ድም ለቅዱሳን ጸሎት መልስ ይሰጣል ። ዕብ ፪ ፡ ፬ - ፭ ።
እግዚአብሔር በበጎ ምግባር ሁሉ የሚወዱትን እን ፳፰
ደሚረዳቸው እናውቃለን ። ዘፍ ፶ ፡ ፳ ።
አስቀድሞ የመረጣቸውንና የወደዳቸውን እነሱን ፳፱
ልጁን ይመስሉ ዘንድ አዘጋጅቷቸዋልና በኵር
እርሱ በብዙ ወንድሞች ላይ ይሆን ዘንድ ። ቈላ ፩ ፡
፲፭ - ፲፬ ። መዝ ፩ ፡ ፮ ። ኤር ፳ ፡ ፭ ። ዕብ ፩ ፡ ፮ ።
ያዘጋጃቸውን እነሱን ጠራ የጠራቸው እነሱን አጸደቀ ፴
የአጸደቃቸው እነሱን አከበረ ። ዕብ ፱ ፡ ፲፭ ።
እንግዲህ ስለዚህ ምን እንላለን? እግዚአብሔር ፴፩
ከእኛ ጋር ከሆነ ማን ይችለናል ። መዝ ፻፲፰ ፮ ።
ዘኍል ፲፬ ፡ ፱ ።
ከኛ ይልቅ ለልጁ ስንኳ አላዘነም ፡ ስለ ሁላችን ቤዛ ፴፪
አድርጎ አሳልፎ ሰጠው እንጂ ፡ እንግዲህ ከሁሉ የማ
ይሰጠን ምን አለ? ዮሐ ፫ ፡ ፲፯ ።
እርሱ ካጸደቀ እንግዲህ እግዚአብሔር የመረጣቸ ፴፫
ውን ሰዎች የሚቋቋማቸው ማነው? ኢሳ ፶ ፡ ፰ - ፱ ።
እርሱ ሲያጸድቅ የሚፈርድ ማነው? ክርስቶስ ኢየ ፴፬
ሱስ ሙቶ ከሙታን ተለይቶ ተነሥቶ በአብ ዕሪና
ተቀምጧል ስለ እኛም ይፈርዳል ።

## ክፍል ፴፮ ፡ ስለ ሰማዕታት ።

የክርስቶስን ፍቅር ማን ያስተወናል መከራ ነውን? ፴፭
ችግር ነውን? ስደት ነውን? ረኀብ ነውን? እርዛት
ነውን? ሾተል ነውን? ጭንቅ ነውን? ዮሐ ፲ ፡ ፳፰።
መጽሐፍ "አንተን ስለ አመነ ዘወትር ይገድሉናል ፴፮
እንደሚታረዱ በጎችም ሁነናል" እንዳለ ። መዝ ፵፬ ፡
፳፪ ። ፪ ቆሮ ፬ ፡ ፲፩ ።

፴፯ ወበሕቱ በእንተዝ ንመውዕ ለኵሉ እስመ ውእቱ
አፍቀረነ ።
፴፰ እትአመን ባሕቱ ከመ አልቦ ዘያኀድገነ ፍቅሮ ለእግ
ዚአብሔር በኢየሱስ ክርስቶስ እግዚእነ ፡ ኢሞት ፡
ወኢ ሕይወት ፡ ኢ መላእክት ፡ ወኢ ቀደምት ፡
ኢ ዘሀሎ ፡ ወኢ ዘይመጽእ ።

፴፱ ኢ ዘኀይል ፡ ወኢ ዘልዑል ፡ ኢ ዘጸድፍ ፡ ወኢ
ዳግም ልደት ዘመትሕት ፡ አልቦ ዘይክል አኀድጎተነ
ፍቅሮ ለክርስቶስ ።

ምዕራፍ ፱ ።

ክፍል ፴ወ፯ ፡ በእንተ ልደቱ ለክርስቶስ እምአበው ።

፩ አማን እብለክሙ በእንተ ክርስቶስ ወኢይሔሱ ወስ
ምዕየ መንፈስ ቅዱስ ዘውስተ ልብየ ።

፪ ከመ እቴክዝ ወአሐምም በልብየ ፈድፋደ በኵሉ
ጊዜ ።
፫ ወእጼሊ ከመ አነ እትዐለል እምክርስቶስ በእንተ
አኀውየ ወአዝማድየ እለ በሥጋ ።
፬ እሉ እሙንቱ እስራኤል እስራኤላውያን እለ ሎሙ
ትርሲተ ወልድ ወሎሙ ክብር ፡ ወሎሙ ሥርዓት ፡
ወሎሙ ሕግ ፡ ወሎሙ አሰፈወ ።

፭ ወእሙንቱ አበዊነ ወእምላዕሌሆሙ ተወልደ ክርስ
ቶስ በሥጋ ሰብአ ዘውእቱ አምላክ ቡሩክ ለዓለመ
ዓለም አሜን ።

፮ አኮ ኢተሐሰወ ቃለ እግዚአብሔር ወአኮ ኵሎሙ
እስራኤል እስራኤላውያን ።

ክፍል ፴ወ፰ ፡ በእንተ ተሰምዮ ዘርአ አብርሃም ።

፯ ወአኮ ኵሎሙ ዘርአ አብርሃም ዘኮንዎ ውሉደ እም
ይስሐቅ ዳእሙ ይሰመይ ለከ ዘርእ ይቤሎ ።

፰ እስመ አኮ ውሉደ ሥጋ እሙንቱ አላ ውሉደ እግ
ዚአብሔር እለ ይከውንዎ ዘርአ እለ አሰፈወ ይኩ
ንዎ ውሉደ ።
፱ እስመ አሰፈዎ ወይቤሎ ዓመ ከመ ዮም እገብእ
ኀቤከ ወትረክብ ሣራ ወልደ ።

፲ ወአኮ ባሕቲታ ዓዲ ርብቃኒ ፀንሰት መንታ ለይስ
ሐቅ አቡነ ።
፲፩ ወዘእንበለ ይትወለዱ ወይግበሩ ሠናየ ወእኩየ ከመ
ይትዐወቅ በምንት እንከ ኅርዮቱ ለእግዚአብሔር ።



ነገር ግን እርሱ ወዶናልና ስለዚህ ሁሉን ድል እንነ ፴፯
ሣቀለን ። ፩ ቆሮ ፲፭ ፡ ፶፯ ። ፩ ዮሐ ፭ ፡ ፬ ።
ነገር ግን በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ያገኘነውን ፴፰
የእግዚአብሔር ፍቅር የሚያስተወን እንደሌለ አም
ናለሁ ፡ ሞትም ቢሆን ፡ ሕይወትም ቢሆን ፡ አለቆችም
ቢሆኑ ፡ የቀደሙትም ቢሆኑ ፡ ያለውም ቢሆን ፡ የሚ
መጣውም ቢሆን ። ቈላ ፩ ፡ ፲፮ ። ፪ ጢሞ ፩ ፡ ፲፪ ።
የኃይል ሥራም ቢሆን ፡ ከፍተኛም ቢሆን ፡ ገደል ፴፱
ቢጥሉን ፡ በዚህ ዓለም የሚነሣ አዲስ ፍጥረትም
ቢሆን የክርስቶስን ፍቅር ሊያስተወን የሚችል
የለም ። ዮሐ ፲ ፡ ፲፰ ። ፪ ቆሮ ፲ ፡ ፭ ።

ምዕራፍ ፱ ፡

ክፍል ፴፯ ፡ ክርስቶስ ከአበው ስለ መወለዱ ።

ስለ ክርስቶስ እውነቱን እነግራችኋለሁ ሐሰት አልና ፩
ገርም ፡ ምስክሬም በልቡናዬ አድሮ ያለ መንፈስ
ቅዱስ ነው ። ምዕ ፩ ፡ ፱ ።
በጊዜው ሁሉ ፈጽሜ በልቤ እንደማዝን እንደምቈ ፪
ረቈር ። ምዕ ፲ ፡ ፳ ።
በሥጋ ዘመዶቼ ፡ ወንድሞቼ ስለሚሆኑ ሰዎች ከክር ፫
ስቶስ ልለይ እጸልያለሁ ። ዘፀአ ፴፪ ፡ ፴፪ ።
እሊህም እስራኤል ተብለው የሚጠሩት የእስራኤል ፬
ወገኖች ናቸው ፡ የልጅነት ክብር ያላቸው ፡ ክብር
ያላቸው ሥርዓት ያላቸው ፡ ሕግ ያላቸው ፡ ተስፋ የተ
ሰጣቸው ። ዘፀአ ፬ ፡ ፳፪ ። ዘዳ ፯ ፡ ፮ ።
እነሱም አባቶቻችን ናቸው ፡ ክርስቶስ በሥጋ ከነሱ ፭
ተወለደ ፡ ይኸውም ለዘለዓለም ምስጋና የሚገባው
አምላክ ነው ፡ በውነት ። ማቴ ፩ ፡ ፩-፳፫ ። ሉቃ ፫ ፡
፳፫-፴፰ ። ዮሐ ፩ ፡ ፩-፳፫ ።
የእግዚአብሔር ቃል አልታበለምና እስራኤል ሁሉ ፮
እስራኤላውያን አይደሉም ። ምዕ ፪ ፡ ፳፰ ። ዘኍ ፳፫ ፡
፲፱ ። ዮሐ ፰ ፡ ፴፱ ።

ክፍል ፴፰ ፡ የአብርሃም ልጅ ስለ መባል ።

ግን የአብርሃም ልጆች ሁሉ ልጆቹ የሆኑ አይደለም ፡ ፯
ከይስሐቅ ዘር ይጠራልሃል አለው እንጂ ። ዘፍ ፳፩ ፡
፲፪ ። ዕብ ፲፩ ፡ ፲፰ ።
እነሱ ሥጋውያን ልጆች አይደሉምና ልጆች እንዲ ፰
ሆኑት ተስፋ ያናገረለት የእግዚአብሔር ልጆች
ናቸው እንጂ ። ገላ ፬ ፡ ፳፫ ።
ከርሞ እንደ ዛሬ ወዳንተ እመለሳለሁ ፡ ሣራም ወንድ ፱
ልጅ ታገኛለች ብሎ ተስፋውን እንደ ነገረው ። ዘፍ
፲፰ ፡ ፲ ።
ሣራ ብቻ አይደለችም ርብቃም ለአባታችን ለይስ ፲
ሐቅ መንታ ፀነሰች እንጂ ። ዘፍ ፳፭ ፡ ፳፩ ።
ሳይወለዱ ክፉና መልካም ሥራም ሳይሠሩ የእግዚ ፲፩
አብሔር ምርጫው በምን እንደሆነ ይታወቅ ዘንድ ።

## ኀበ ሰብአ ሮሜ ፱ ።

፲፪ ከመ ያእምሩ ከመ ኢኮነ በምግባሩ ለሰብእ ዘእንበለ ዳእሙ ዘውእቱ ጸውዐ ወይቤላ ለርብቃ ዘየዓቢ ይትቀነይ ለዘይንእስ ።
፲፫ እስመ ከማሁ ጽሑፍ ያዕቆብሃ አፍቀርኩ ወኤሳውሃ ጸላእኩ ።

### ክፍል ፴ወ፱ ፡ በእንተ ኢመፍትው ሐቲተ ፍትሑ ።

፲፬ ምንተ እንከ ንብል ይዔምፅኑ እግዚአብሔር ፡ ሐሰ ።
፲፭ ወይቤሎ እግዚአብሔር ለሙሴ ለዘሂ መሐርክዎ እምሕሮ ወለዘሂ ተሣሀልክዎ እሣሀሎ ።
፲፮ ናሁኬ ኢኮነ ለዘበደረ ወለዘሮፀ ዘእንበለ ዳእሙ ለዘእግዚአብሔር ምሕሮ ።
፲፯ ወይቤሎ እግዚአብሔር በመጽሐፍ ለፈርዖን በእንተዝ አንሣእኩከ ከመ አርኢ ኀይልየ በላዕሌከ ወይሰማዕ ስምየ በኵሉ ምድር ።
፲፰ ናሁኬ ለዘፈቀደ ይምሕር ወለዘፈቀደ ያበዕብ ።
፲፱ ምንተ ትብል ተሐይሰኑ ለእግዚአብሔር በኑ ዘይትቃወማ ለምክሩ ።
፳ እጓለ እመሕያው ምንትኑ አንተ ዘትትዋሥኦ ለእግዚአብሔር ፡ ይክል ኑብሂሎቶ ግብር ለገባሪሁ ኢትግበረኒ ከመዝ ።
፳፩ ኢኮነኑ ብዉሐ ለብሐዊ ይግበር እምአሐዱ ጽቡር ንዋየ ፡ መንፈቆ ለክብር ወመንፈቆ ለኀሣር ።
፳፪ ወእመኒ ፈቀደ እግዚአብሔር ያርኢ መቅሠፍተ ኀይሉ አርእዮ ትዕግሥቶ ያመጽእ መላእክተ መዓቱ እለ ድልዋን ለአማስኖ ።
፳፫ ወከመ ያርኢ ክዕበ ብዕለ ስብሐቲሁ ያመጽእ መላእክተ ምሕረቱ እለ ድልዋን ለሣህል ላዕለ እለ ጸውዐ ወአቅደመ አእምሮ ።

### ክፍል ፵ ፡ በእንተ ጽዉዓን ።

፳፬ ወንሕነ እሙንቱ እለ ጸውዓነ ውስተ ክብሩ ወአስተጋብአነ አኮ እምአይሁድ በሕቲቶሙ ዓዲ እምአረሚ ።
፳፭ በከመ ይቤ ሆሴዕ ነቢይ እሬስዮ ሕዝብየ ለዘኢኮነ ሕዝብየ ወእሬስያ ፍቅርትየ ለእንተ ኢኮነት ፍቅርትየ ።
፳፮ ወይከውኑ ውሉደ እግዚአብሔር ሕያው በብሔር በኀበ ይቤልዎሙ ኢኮንክሙ ሕዝበ እግዚአብሔር።
፳፯ ኢሳይያስኒ ከልሐ ወይቤ በእንተ እስራኤል ለእመ ከነ ኍልቆሙ ለደቂቀ እስራኤል ከመ ኆፃ ባሕር እለ ተርፉ ይድኅኑ ።

## ወደ ሮሜ ሰዎች ፱ ።

እርሱ የመረጠው ነው እንጂ ፡ ሰው በሥራው የሚመረጥ እንዳይደለ ያውቁ ዘንድ ፡ ርብቃን ታላቁ ለታናሹ ይገዛል አላት ። ዘፍ ፳፭ ፡ ፳፫ ። ፲፪
"ያዕቆብን ወደድኩ ኤሳውን ጠላሁ" ተብሎ እንዲሁ ተጽፎአልና ። ሚል ፩ ፡ ፪ - ፫ ። ፲፫

### ክፍል ፴፱ ፡ ፍርዱን መመራመር ስለማይገባ ።

እንግዲህ ምን እንላለን ፡ እግዚአብሔር ያደላልን ? አያደላም ። ፲፬
እግዚአብሔር ሙሴን የምምረውን እምረዋለሁ ይቅር የምለውንም ይቅር እለዋለሁ ፡ አለው ። ዘፀአ ፴፫ ፡ ፲፱ ። ፲፭
እነሆ ለሮጠ ለቀደመ አልሆነም ፡ እግዚአብሔር ይቅር ላለው ነው እንጂ ። ኤፌ ፪ ፡ ፰ ። ፲፮
"እግዚአብሔር ፈርዖንን በነገር እንዲህ አለው ፡ ኃይሌን በአንተ ላይ እገልጥ ዘንድ ስሜም በምድር ሁሉ ይሰማ ዘንድ" ። ዘፀአ ፱ ፡ ፲፮ ። ፲፯
እነሆ የወደደውን ይምራል ፡ የወደደውን ይቀጣል ። ፲፰
ምን ትላለህ? አንተ እግዚአብሔርን ትነቅፈው ይሆን? የእግዚአብሔርንስ ምክሩ የሚቃወማት አለን? ኢዮ ፱ ፡ ፲፮ ። ፲፱
የሰው ልጅ ፡ እግዚአብሔርን ለምን ትከራከረዋለህ? ሥራ ሠሪውን እንዲህ አድርገህ አትሥራኝ ሊለው ይችላልን? ኢሳ ፳፱ ፡ ፲፮ ። ኢሳ ፵፭ ፡ ፱ ። ፳
ሸክላ ሠሪ ከአንድ ጭቃ ዕቃውን ግማሹን ለክብር ግማሹን ለኃሣር ሊሠራ አይችልምን? ። ኤር ፲፰ ፡ ፮። ፪ ጢሞ ፪ ፡ ፳ ። ፳፩
እግዚአብሔር ኃይሉን የሚገልጽበትን ቀጣቱን ሊያሳይ ቢወድ ትዕግሥቱን ካሳየ በኋላ ለማጥፋት የተዘጋጁትን ቍጣውን የሚገልጽበት መላእክትን ያመጣል ። ምሳ ፪ ፡ ፬ ። ፪ ጴጥ ፪ ፡ ፱ ። ፳፪
ዳግመኛም የጌትነቱን ብዛት ሊያሳይ ቢወድ አስቀድሞ መርጦ በወደዳቸው ለይቅርታ የተዘጋጁ የይቅርታ መላእክትን ያመጣል ። ኤፌ ፩ ፡ ፫ - ፲፪ ። ፳፫

### ክፍል ፵ ፡ ስለ ተጠሩት ።

ወደ ክብሩ የጠራን የሰበሰበን እኛ ነን ከአይሁድ ብቻ አይደለም ፡ ከአረማውያንም እንጂ ። ፳፬
ነቢይ ሆሴዕ እንዲህ እንዳለ "ወገኔ ያልነበረውን ወገኔ አደርገዋለሁ ፡ ወዳጄ ያልነበረችውንም ወዳጄ አደርጋታለሁ" ። ፳፭
የእግዚአብሔር ወገኖች አይደላችሁም ይሏቸው በነበሩት አገር የእግዚአብሔር ልጆች ይሆናሉ ። ሆሴ ፩ ፡ ፱ ። ኢሳ ፷፭ ፡ ፩ ። ፳፮
ኢሳይያስም ድምፁን ከፍ አድርጎ ስለ እስራኤል እንዲህ አለ ፡ "የእስራኤል ልጆች ቍጥራቸው እንደ ባሕር አሸዋ ቢሆን የተረፉት ይድናሉ ። ምሳ ፲፩ ፭ ። ፳፯

፳፰ እስመ ኍሉቀ ወምቱረ ነገረ ይነግር እግዚአብሔር ውስተ ዓለም ዘሀለዎ ይግበር ።
፳፱ ወበከመ አቅደመ ኢሳይያስ ብሂለ ሶበ አኮ እግዚአብሔር ፀባዖት ዘአትረፈ ለነ ዘርአ ከመ ሰዶም እምኮነ ወከመ ገሞራ እመሰልነ ።

ክፍል ፶ወ፩ ፡ በእንተ ጽድቀ ሃይማኖት ።

፴ ምንተ እንከ ንብል አረሚ ጥቀ እለ ኢኀሠሥዋ ለጽድቅ ረከብዋ ለጽድቅ ፡ ወጸድቁ በአሚን ።
፴፩ ወእስራኤልሰ እንዘ ይዴግንዋ ለኦሪቶሙ ስእኑ ጸዲቀ እስመ ኢፈጸሙ ገቢረ ሕገገ ኦሪቶሙ ።
፴፪ በእንተ ምንት እስመ ኢኮነ ጽድቆሙ በአሚን ዘእንበለ ዳእሙ በገቢረ ሕገገ ኦሪት ወእዕቀፈቶሙ እብነ ዕቅፍት ።
፴፫ እስመ ከማሁ ይቤ መጽሐፍ ናሁ እነብር ውስተ ጽዮን እብነ ዕቅፍት ወእብነ ጌጋይ ወዘአምነ ባቲ ኢይትኃፈር ለዓለም ።

ምዕራፍ ፲ ።

ክፍል ፶ወ፪ ፡ በእንተ ፈቃዱ ለጳውሎስ ።

፩ አኀውየ ሊተሰኬ ፈቃደ ልብየኒ ወጸሎትየኒ ከመ ይሕየዉ ኵሉ እስራኤል ።
፪ እስመ አነ ማሕተቶሙ ከመ ይቅንኡ ለእግዚአብሔር ወአኮሰ በአእምሮቶሙ ።
፫ እስመ ኢየአምርዋ ለጽድቀ እግዚአብሔር ወፈቀዱ በጽድቀ ርእሶሙ ይቁሙ ወለጽድቀ እግዚአብሔርሰ ስእኑ ገንየ ።
፬ ወማኅለቅቱሰ ለጽድቀ ኦሪት አሚን በክርስቶስ ውእቱ ፡ ለኵሎሙ እለ የአምኑ ቦቱ ።

ክፍል ፶ወ፫ ፡ በእንተ ዘይቤ ሙሴ ።

፭ ወሙሴኒ ይቤ ኵሉ ዘፈጸመ ገቢረ ሕገገ ኦሪት ይጸድቅ ቦቱ ።
፮ ወጽድቀ አሚንሰ ከመዝ ይብል ኢትበል በልብከ ፡ መኑ የዐርግ ሰማየ ክርስቶስ ውእቱ ዘወረደ እምሰማይ ።
፯ ወመኑ ይወርድ ውስተ ቀላይ ፡ ክርስቶስ ውእቱ ዘተንሥአ እሙታን ።
፰ አኮኑ ከማሁ ይቤ መጽሐፍ ቅሩብ ለከ ቃል ውስተ አፉከ ወውስተ ልብከ ወዝ ውእቱ ቃለ ዘእሜሀረክሙ።
፱ እምከመ ተአምን በአፉከ ከመ ክርስቶስ ውእቱ እግዚእ ወተአምን በልብከ ከመ አንሥአ እግዚአብሔር እምዉታን ተሐዩ ።



እግዚአብሔር በዓለም ውስጥ ያደርገው ዘንድ ያለ ፳፰
ውን ያለቀ የተቈረጠ አድርጎ ይናገራልና ። አሞ ፫ ፡ ፯ ።
ኢሳይያስም አስቀድሞ እንደ ተናገረ ፡ "አሸናፊ እግ ፳፱
ዚአብሔር ዘር ያስቀረልን ባይሆን ኖሮ ፡ እንደ ሰዶም በሆን ገሞራንም በመሰልን ነበር" ። ኢሳ ፩ ፡ ፱ ። ዘፍ ፲፱ ፡ ፳፬ ።

ክፍል ፶፩ ፡ በሃይማኖት ስለ መጽደቅ ።

እንግዲህ ምን እንላለን ? ጽድቅን ያልፈለጓት አረማ ፴
ውያን እንኳ ጽድቅን አገኟት በሃይማኖትም ጸደቁ ።
እስራኤል ግን ኦሪትን ሲከተሉ መጽደቅ ተሳናቸው ፴፩
የኦሪታቸውን ሕግ ሥራ አልፈጸሙምና ። ምዕ ፲ ፡ ፪ ።
ስለምን ? ጽድቃቸው የኦሪትን ሕግ በመሥራት ፴፪
እንጂ በሃይማኖት አልሆነምና የዕንቅፋት ደንጊያ አሰነካከላቸው ። ሉቃ ፪ ፡ ፴፬ ። ፩ ቆሮ ፩ ፡ ፳፫ ።
እንዲሁ መጽሐፍ "እነሆ በጽዮን የዕንቅፋት ደን ፴፫
ጊያ የበደል ደንጊያ እኖራለሁ ፡ ያመነበት ለዘላለም አያፍርም" ብሏልና ። ኢሳ ፰ ፡ ፲፬ ። ፳፰ ፡ ፲፯ ።

ምዕራፍ ፲ ።

ክፍል ፶፪ ፡ ስለ ጳውሎስ ፈቃድ ።

ወንድሞቼ ! እኔስ የልቤም ምኞት ጸሎቴም እስራ ፩
ኤል ሁሉ እንዲድኑ ነው ።
ለእግዚአብሔር እንደሚቀኑ ምስክራቸው እኔ ነኝ ፪
ግን ዐውቀው አይደለም ። ፪ ነገ ፲ ፡ ፲፮ ። ፊል ፫ ፡ ፮ ።
የእግዚአብሔርን ጽድቅ አያውቋትምና በራሳቸው ፫
ጽድቅ ፀንተው ሊኖሩ ወደዱ ፡ ለእግዚአብሔር ጽድቅ ግን መገዛት ተሳናቸው ። መዝ ፸፩ ፡ ፲፭ - ፲፮ ።
የኦሪት ጽድቅ ፍጻሜው ግን በክርስቶስ ማመን ነው። ፬
ይኸውም ላመኑበት ሁሉ ነው ። ማቴ ፭ ፡ ፲፯ ። ዕብ ፰ ፡ ፲፫ ። ዮሐ ፫ ፡ ፲፰ ።

ክፍል ፶፫ ፡ ሙሴ ስለ ሰጠው ትእዛዝ ።

ሙሴም የኦሪትን ሕግ መሥራትን የፈጸመ ሁሉ ይከ ፭
ብርበታል አለ ። ዘሌ ፲፰ ፡ ፭ ። ገላ ፫ ፡ ፲፪ ።
የሃይማኖት ጽድቅ ግን እንዲህ ይላል ፡ በልቡናህ ፮
ወደ ሰማይ ማን ይወጣል ? አትበል ፡ ከሰማይ የወረደው ክርስቶስ ነው ። ዘዳ ፴ ፡ ፲፪ - ፲፫ ። ዕብ ፰ ፡ ፩ ።
ወደ ጥልቁስ ማን ይወርዳል? አትበል ፡ ከሙታን ተለ ፯
ይቶ የተነሣው ክርስቶስ ነው ። ምዕ ፬ ፡ ፳፭ ። ፩ ቆሮ ፲፭ ፡ ፫ - ፬ ።
እንዲሁ መጽሐፍ "ቃል ለልብህም ለአፍህም ቀርበ ፰
ልሃል" ይል የለምን ? የማስተምራችሁ ቃል ይህ ነው ። ዘዳ ፴ ፡ ፲፬ ። ፩ ጢሞ ፬ ፡ ፮ ።
ክርስቶስ የባሕርይ አምላክ እንደሆነ በአፍህ ብታ ፱
ምን እግዚአብሔርም ከሙታን ለይቶ እንደ አስነሣው ም በልብህ ብታምን ትድናለህ ። ፪ ቆሮ ፬ ፡ ፭ ።

፲ ወልብኒ ዘየአምን በቱ ይጸድቅ ወአፍኒ ዘየአምን
በቱ የሐዩ ።
፲፩ ወይቤ መጽሐፍ ኵሉ ዘየአምን በቱ የሐዩ ።

፲፪ ኢፈለጠ ወኢሌለየ አይሁዳዌ ወአረማዌ እስመ
ባዕል እግዚአብሔር ወየአክል ለኵሉ ዘጸውዖ ።

፲፫ እስመ ኵሉ ዘጸውዐ ስመ እግዚአብሔር የሐዩ ።

ክፍል ፶ወ፬ ፡ በእንተ እለ ይጼውዑ ስመ እግዚአብሔር ።

፲፬ ወበሕቱ እፎ ይጼውዕዎ እንዘ ኢየአምኑ በቱ ፡ ወእፎ
የአምኑ በዘኢሰምዑ ።
፲፭ ወእፎኑ ይሰምዑ ዘኢሰበኩ ሎሙ ወእፎኑ ይሰብኩ
ሎሙ ዘኢተፈነወ ሐዋርያ ኀቤሆሙ በከመ ይቤ
መጽሐፍ ሠናይ እገሪሆሙ ለእለ ይዜንዉ ሠናየ ዜና።

፲፮ ወበሕቱ አኮ ኵሎሙ ዘሰምዑ ትምህርተ ወንጌል
አኮኑ ኢሳይያስኒ ይቤ እግዚኦ መኑ የአምነነ ቃለነ
ወስምዓነ ወለመኑ ተከሥተ መዝራዕቱ ለእግ
ዚአብሔር ።
፲፯ ወአሚንሰ እምሰሚዕ፡ ወእምሰሚዕ አሚን በቃለ
እግዚአብሔር ክርስቶስ ።
፲፰ ወበሕቱ እብል ቦኑ ኢሰምዑ እስራኤል አኮኑ ይቤ
መጽሐፍ ውስተ ኵሉ ምድር ወፅአ ነገሮሙ ወእስከ
አጽናፈ ዓለም በጽሐ ነቢቦሙ ።

፲፱ እስራኤልኑ ዳእሙ ኢሰምዑ አኮኑ ሙሴሂ አቅደመ
ብሂሎቶሙ አነ አቀንአሙ ለሕዝብ በዘኢይሌብዉ
ወአምዕዖሙ በዘኢኮነ ሕዝብ ።

፳ ኢሳይያስኒ ተሀቢሎ ይቤ ረከቡኒ እለ ኢኀሠሡኒ
ወአስተርአይክዎሙ ለእለ ኢተስእሉኒ ።
፳፩ ወለእስራኤልሰ ይቤሎሙ ኵሎ ዕለተ አንሥእ እደ
ውየ ኀበ ሕዝብ ዐላውያን ወከሐድያን ።

ምዕራፍ ፲ወ፩ ።

ክፍል ፶ወ፭ ፡ በእንተ ሕዝበ እስራኤል።

፩ እብል እንከ ገደፎሙኑ እግዚአብሔር ለሕዝቡ ሐሰ ፡
አኮኑ አነ እስራኤላዊ አነ ዘርአ አብርሃም እምሕ
ዝበ ብንያም ።

፪ ኢገደፈ እግዚአብሔር ሕዝቦ ዘአቅደመ አእምሮ
ኢተአምርኑ ዘይቤ ኤልያስ አመ ሰከዮሙ ለእስራ
ኤል ኀበ እግዚአብሔር እንዘ ይብል ።
፫ እግዚኦ ነቢያቲከኒ ቀተሉ ወምሥዋዒከኒ ነሠቱ
ወአነ ባሕቲትየ ተረፍኩ ወየኀሥሥዋ ለነፍስየ ።

ወደ ሮሜ ሰዎች ፲፩ ።

ያመነበት ልብ ይከብራል ፡ ያመነበት አፍም ይድ ፲
ናል ። መዝ ፻፲፮ ፡ ፩ ።
መጽሐፍም "ያመነበት ሁሉ ይድናል" ብሏል ። ኢሳ ፲፩
፳፰ ፡ ፲፮ ። መዝ ፳፭ ፡ ፫ ።
አይሁዳዊ አረማዊ ብሎ አልለየም እግዚአብሔር ፲፪
ባለ ጸጋ ነውና ፡ ለለመነውም ሁሉ ይበቃልና። ግብ
ሐዋ ፲ ፡ ፴፬ ። ግብ ሐዋ ፲፭ ፡ ፱ ።
የእግዚአብሔርን ስም የጠራ ሁሉ ይድናልና ። ኢዩ ፲፫
፪ ፡ ፴፪ ። ግብ ሐዋ ፪ ፡ ፳፩ ።

ክፍል ፶፬ ፡ የእግዚአብሔርን ስም ስለሚጠሩ ።

ግን ሳያምኑበት እንዴት ይጠሩታል ? ባልሰሙትስ ፲፬
እንዴት? ያምናሉ ። ቲቶ ፩ ፡ ፫ ።
ያልሰበኩላቸውንስ እንዴት ይሰማሉ ? ሐዋርያ ፲፭
ተሹሞ ያልተላከላቸውስ እንዴት ይሰብኩላቸዋል? ፡
"የመልካም ምሥራች ነገር የሚናገሩ ሰዎች አመጣ
ጣቸው መልካም ነው" ብሎ መጽሐፍ እንደተናገረ።
ግን ሁሉም የወንጌልን ትምህርት የሰሙ አይደለም ፲፮
ኢሳይያስም አለ "አቤቱ ቃላችንን ምስክርነታችን
ንስ ማን ያምነናል ? የእግዚአብሔርስ ክንዱ ለማን
ተገለጠ ?" ኢሳ ፶፫ ፡ ፩ ። ዮሐ ፲፪ ፡ ፴፰ ።
ማመን ከመስማት ነው ፡ ከመስማትም በእግዚአብ ፲፯
ሔር ቃል በክርስቶስ ማመን ይገኛል ። ዮሐ ፲፯ ፡ ፳።
ግን እንዲህ እላለሁ፡ በውኑ እስራኤል ብቻ አልሰ ፲፰
ሙምን ? መጽሐፍ "ነገራቸው በምድር ሁሉ ተሰማ ፡
ቃላቸውም እስከ ዓለም ዳርቻ ደረሰ" ብሎ የለምን?።
መዝ ፲፱ ፡ ፬ - ፭ ። ኢሳ ፶፱ ፡ ፯ ። ቈላ ፩ ፡ ፳፫ ።
እስራኤል ብቻ አልሰሙምን ? ሙሴስ አስቀድሞ እን ፲፱
ዲህ ብሏቸው የለምን ? እኔ በማያስተውሉ ወገኖች
አስቀናቸዋለሁ ፡ ወገን ባልሆነውም አስቈጣቸዋለሁ ።
ዘዳ ፴፪ ፡ ፳፩ ።
ኢሳይያስም ደፍሮ "ያልፈለጉኝ አገኙኝ ፡ ላልጠየቁ ፳
ኝም ተገለጥኩላቸው" ብሎ የለምን ? ኢሳ ፷፭ ፡ ፩ ።
እስራኤልን ግን ሁልጊዜ ከዳተኞች ወንጀለኞች ፳፩
ወደሆኑት ሕዝብ እጄን እነሣለሁ ብሏቸው የለምን?።

ምዕራፍ ፲፩ ፤

ክፍል ፶፭ ፡ ስለ እስራኤል ሕዝብ ።

እንግዲህ እንዲህ እላለሁ ፡ እግዚአብሔር ወገኖቹን ፩
ጣላቸውን ? አልጣላቸውም ፤ እኔ ከብንያም ወገን
የምሆን የአብርሃም ዘር እስራኤላዊ አይደለሁምን?
ኤር ፴፩ ፡ ፴፯ ። ፊል ፫ ፡ ፬ - ፲ ።
እግዚአብሔር አስቀድሞ የወደዳቸውን ሕዝቡን አል ፪
ጣለም ኤልያስ እስራኤልን ወደ እግዚአብሔር በከሰ
ሳቸው ጊዜ ያለውን አታውቅምን ፡ እንዲህ ብሎ ።
አቤቱ ፣ ነቢያትህን ገደሉ መሠዊያህንም አፈረሱ እኔ ፫
ብቻዬን ቀረሁ ፡ ነፍሴንም ይሿታል ። ፩ነገ ፲፱ ፡ ፲ - ፲፬።

፬ ወምንተ ይቤሎ ዘአስተርአዮ አትረፍኩ ሊተ ሰብዓ
ምእተ ብእሴ እለ ኢያምለክዎ ለበዓል ።
፭ ከማሁኬ ዮምኒ በዝ መዋዕል እምእለ ኮኑ ኅሬ
በጸጋ እለ ተርፉ አምኑ በእግዚአብሔር ።

## ክፍል ፶ወ፮ ፡ በእንተ ኅሬ ።

፮ ወእመሰኬ በጸጋ ጸድቁ ኢኮነኬ በጽድቀ ምግባሮሙ
ወእመ አኮሰ ጸጋ ኢይከውን ጸጋ ለእመ በምግባር
ይጸድቁ ።
፯ ምንተ እንከ የኀሥሥ እስራኤል ዘዘንተ ኢያድምዐ
ወኅሬሰ አድምዐ ወእለሰ ተርፉ ፆሩ ።

፰ በከመ ይቤ መጽሐፍ ወሀበሙ እግዚአብሔር መን
ፈሰ ድንዙዘ ከመ ኢይነጽሩ በአዕይንቲሆሙ ወኢ
ይርአዩ ወኢይስምዑ በዕዘኒሆሙ እስከ ዮም ።
፱ ዳዊትኒ ይቤ ለትኩኖሙ ማእዶሙ መሥገርተ በቅድ
ሜሆሙ ለፍዳሆሙ ወለዕቅፍቶሙ ።

፲ ይጽለማ አዕይንቲሆሙ ወኢይርአያ ወይትቀፃዕ ዘባ
ናቲሆሙ በኵሉ ጊዜ ።
፲፩ እብል እንከ ተዐቅፉኑ ከመ ይደቁ ሐሰ ፡ አኮኑ በእ
ንተ ተዐቅፎቶሙ ኮነ ሕይወት ላዕለ አሕዛብ ከመ
ይቅንኡ ።
፲፪ ሶበ ስሒተ ዚአሆሙ ሣህለ ኮነ ለአሕዛብ ወኄጋየ
ዚአሆሙ ብዕለ ኮነ ለዓለም እፎ እንጋ እምኮነ
ፍጻሜሆሙ ።

## ክፍል ፶ወ፯ ፡ በእንተ አሕዛብ ።

፲፫ ለክሙ እብል ለአሕዛብ እምጣነሰ ሐዋርያሆሙ አነ
ለአሕዛብ እሴብሓ ለመልእክትየ ።

፲፬ እመቦ ከመ አቅንአሙ በዝንቱ ለአዝማድየ ወለሕዝ
ብየ ወአድኅን እለ ኮኑ እምኔሆሙ ።

፲፭ እስመ ፀአተ ዚአሆሙ ሣህለ ኮነ ለዓለም እፎ ፈድ
ፋደ እምኮነ ተመይጦቶሙ ሕይወት እሙታን ።

፲፮ ወለእመ ኮነት ቀዳሚሃ ቅድስተ ወብኍእኒ ቅዱስ
ከማሁ ፡ ወለእመ ኮነ ሥርዋ ቅዱሰ ከማሁ አዕፁቂ
ሃኒ ቅዱስ ።
፲፯ ወለእመ ተሰብሩ እምአዕፁቂሃ ኪያከ አውልዐ
ገዳም ተከሉ በመከኖሙ ወኀበርከ ሥርወ ምስሌ
ሆሙ ወከንከ ዘይተ ከማሆሙ ።

የታየውስ ምን አለው ? በዓልን ያላመለኩትን ሰባት ፬
ሺሕ ሰዎች አስቀርቻለሁ ። ፩ ነገ ፲፱ ፡ ፲፰ ።
እንዲሁም እስ ዛሬም በዚህ ዘመን በጸጋ የተመረጡ ፭
ከሆኑት ወገን የቀሩት በእግዚአብሔር አምነዋል ።
ምዕ ፱ ፡ ፳፯ ።

## ክፍል ፶፮ ፡ ስለ ምርጫ ።

በጸጋ ከጸደቁ ግን በሥራቸው አይደለማ? ያለዚያስ ፮
በምግባር የሚጸድቁ ከሆነ ጸጋ ፡ ጸጋ አይባልማ ?
ዘዳ ፱ ፡ ፬ - ፭ ።
እንግዲህ ይህን ያልተቀበለ እስራኤል ምን ይሻል ? ፯
የተመረጠው ግን አግኝቷል ፡ የቀሩት ግን ታወሩ ።
ምዕ ፱ ፡ ፴፩ ።
መጽሐፍ እስከ ዛሬ ድረስ በዓይናቸው እንዳያዩ ፡ ፰
በጆሮአቸውም እንዳይሰሙ እግዚአብሔር ሰነፍ አእ
ምሮ ሰጣቸው እንዳለ ። ኢሳ ፮ ፡ ፲ ። ፳፱ ፡ ፲ ።
ዳዊትም እንዲህ ብሏል ፡ ማእዳቸው በፊታቸው ወጥ ፱
መድ ትሁንባቸው ፡ ፍዳ ሊመጣባቸው መሰናከል
ልትሆንባቸው ። መዝ ፷፱ ፡ ፳፫ - ፳፬ ።
እንዳያዩ ዓይኖቻቸው ይጨልሙ ፡ ዘወትር ጀርባ ፲
ቸው ይጕበጥ ።
እንግዲህ ሊወድቁ ተሰናከሉ እላለሁን ? ፡ አልልም ፲፩
እነሱ እንዲቀኑ በመሰናከላቸው ለአሕዛብ ሕይ
ወት ሆኖ የለምን? ። ምዕ ፲ ፡ ፲፱። ግብ ሐዋ ፲፫፡ ፵፮።
የእነሱ መሰሳት ለአሕዛብ ዕርቅ ፡ በደላቸውም ለዓ ፲፪
ለም ክብር ከሆነ ፍጹምነታቸውማ! እንዴት በሆነ? ።
ሆሴ ፩ ፡ ፲ ።

## ክፍል ፶፯ ፡ ስለ አሕዛብ ።

ለእናንተ ለአሕዛብ እነግራችኋለሁ እኔ ለአሕዛብ ፲፫
መምህራቸው እንደመሆኔ መጠን መልእክቴን አገ
ለግላለሁ ።
በዚህ ወገኖቼንና ዘመዶቼን አስቀናቸው እንደሆነ ፲፬
ከነሱ ወገን የሆኑትንም አድን እንደሆነ ። ፩ ጢሞ
፬ ፡ ፲፮ ።
የእነሱ መውጣት ለዓለም ዕርቅ ከሆነ ፡ ይልቁንም ፲፭
ከሙታን ተለይተው እንደመነሣታቸው የሚቈጠር
ከሆነ መመለሳቸውማ እንዴት ሕይወት በሆነ ነበር ? ።
እርሾዩቱ ያማረች ከሆነች ብሆውም እንዲሁ ያማረ ፲፮
ነው ፡ ሥርዋ ያማረ ከሆነ ጫፍዋም እንዲሁ ያማረ
ይሆናል ።
ከጫፎቿ ቢሰበሩ አንተን የምድረ በዳ ወይራ በእ ፲፯
ነሱ ፈንታ ተከሉ ፡ ከእነሱም ጋር በሥር ተባበርክ ፡
እንደነሱም ዘይት ሆንክ ። ኤፌ ፪ ፡ ፲፩ - ፲፱ ። ኤር
፲፩ ፡ ፲፮ ።

## ክፍል ፵ወ፰ ፡ በእንተ ዘኢይደሉ ተዝኅሮ ።

፲፰ ወኢ.ትዘኀር ላዕለ አዕፁቅ ፡ ወእመሰ ተዝኅርከ አኮ
አንተ ዘትፀውሮ ለሥርው አላ ሥርው ይፀውረከ ለከ ።

፲፱ ትብለኑ ተሰብሩ እምአዕፁቂሃ ወእነ ኮንኩ ዐፅቀ
ዘይት ህየንቴሆሙ ።
፳ ርቱዕ ይሰብሩ እስመ ኢአምኑ ወአንተሰ ቆምከ
እስመ አመንከ ፍሩሀከ ንበር እንከ ወኢታዕቢ
ርእሰከ ።
፳፩ ሶበ ለአልክቱ እለ ፍጥረቶሙ ዘይት እሙንቱ ኢመ
ሐኮሙ እግዚአብሔር ኪያከኑ ይምሕከከ ።
፳፪ ርኢ እንከ ምሕረቶሂ ወአጥብዖቶሂ ለእግዚአብሔር
ለእለሰ ወድቁ አውቀዮሙ ወለከሰ ምሕረከ ለእመ
ነበርከ በዘምሕረከ ወእመ አኮሰ ኪያከኒ ያወቅየከ ።

፳፫ ወሎሙኒ ይተክሎሙ ለእመ አምኑ ይክል እግዚአ
ብሔር ተኪሎቶሙ ዳግመ ።
፳፬ ኪያከ ጥቀ አውልዐ ገዳም ገዘመከ እምፍጥረትከ
ወተከለከ ውስተ ዘኢኮነ ፍጥረትከ ውስተ ሠናይ
ዘይት እፎ እንከ ፈድፋደ ሎሙ ይክል ተኪሎቶሙ
ውስተ ፍጥረቶሙ እለ ዘይት እሙንቱ ቀዳሚሆሙ ።

## ክፍል ፵ወ፱ ፡ ምክር በእንተ
## እለ ይቤሉ ጠቢባን ንሕነ ።

፳፭ ወእፈቅድ ለክሙ አኀዊነ ታእምሩ ዘንተ ምክረ
ከመ ኢትበሉ ጠቢባን ንሕነ እስመ ዑረተ ልብ ረከ
በሙ ለእስራኤል መክፈልቶሙ እስከ አመ ይበ
ውኡ ኵሉ አሕዛብ ።
፳፮ ወእምዝ የሐይዉ ኵሎሙ እስራኤል በከመ ይቤ
መጽሐፍ እምጽዮን ይወፅእ መድኅን ወያአትት
ኃጢአተ እምያዕቆብ ።

፳፯ ወበቱ ይረክቡ ተስፋሆሙ አመ አእተትኩ ሎሙ
ኃጢአቶሙ ።
፳፰ እመንገለ ወንጌልሰ ፀርነ እሙንቱ በእንቲአክሙ ወእ
መንገለ ኅሬሰ አኀዊነ እሙንቱ በእንተ አበዊነ ።

፳፱ እስመ አልቦ ንስሐ በጸጋ እግዚአብሔር ።
፴ በከመ አንትሙ ቀዲሙ ዐለውክምዎ ለእግዚአብ
ሔር ወይእዜሰ ተሣሀልክሙ ።
፴፩ ከማሁ እሙንቱሂ ዓለውዎ ይእዜሰ ከመ ሎሙኒ
ይሣሀሎሙ ።
፴፪ እስመ እግዚአብሔር ዘግሐ ለኵሉ ውስተ ኃጢአት
ከመ ይሣሀሎ ለኵሉ ።

## ክፍል ፵፰ ፡ መኵራት ስለማይገባ ።

በአዕፁቅ ላይ አትኵራ ብትኰራ ግን ሥሩ አንተን ፲፰
ይሸከምሀል እንጂ አንተ ሥሩን የምትሸከመው አይ
ደለም ። ዮሐ ፬ ፡ ፳፪ ።
ከጫፎቻ አንዳንዶቹ ተሰበሩ ፡ በእነሱ ፈንታ እኔ የዘ ፲፱
ይት ጫፍ ሆንኩ ትል ይሆን? ። ግብ ሐዋ ፲፫፡ ፵፮።
አላመኑምና ሊሰበሩ ይገባል ፡ አንተ ግን ቆመሃል ፳
አምነሃልና እንግዲህ ፈርተህ ኑር ራስህንም ከፍ
ከፍ አታድርግ ። ፩ ቆሮ ፲ ፡ ፲፪ ።
እግዚአብሔር ፍጥረታቸው ዘይት ለነበረው ለእነ ፳፩
ዚያ ያልራራላቸው ላንተ ይራራልሃልን ? ።
እንግዲህ የእግዚአብሔርን ቸርነቱንና ጭከናውን ፳፪
አስተውል የወደቁትን ቀጣቸው አንተን ግን ይቅር
አለህ ይቅር እንዳለህ ብትኖር መልካም ነው ፡ ያለ
ዚያ ግን አንተንም ይቀጣሃል ። ዮሐ ፲፭ ፡ ፪ - ፬ ።
እነሱንም ይተክላቸዋል ካመኑ እግዚአብሔር ዳግ ፳፫
መኛ ሊተክላቸው ይችላል ። ፪ ቆሮ ፫ ፡ ፲፮ ።
አንተን የምድረ በዳ ወይራ ! አንተ እንኳ ከበቀልክ ፳፬
በት ቈርጦ ባልበቀልክበት በመልካሙ ዘይት ሥፍራ
ተክሎሃል ይልቁንም ጥንቱን ዘይት የነበሩትን እነ
ዚያን በበቀሉት ሥፍራ እንዴት ሊተክላቸው ይችል
ይሆን ? ። ኤር ፲፩ ፡ ፲፮ ።

## ክፍል ፵፱ ፡ እኛ አዋቂዎች ነን
## ለሚሉ ሰዎች የተሰጠ ምክር ።

ወንድሞቻችን ! እኛ አዋቆች ነን እንዳትሉ ይህን ፳፭
ምክር ልታውቁ እወዳለሁ ፡ አሕዛብ ወደ ሃይማኖት
እስኪገቡ ድረስ ከእስራኤል እኩሌቶቹን የልብ ዕዉ
ርነት አግኝቷቸዋልና ። ሉቃ ፳፩ ፡ ፳፬ ። ዮሐ ፲ ፡ ፲፮ ።
ከዚህም በኋላ እስራኤል ይድናሉ መጽሐፍ እንዲህ ፳፮
እንዳለ "አዳኝ ከጽዮን ይወጣል ፡ ከያዕቆብም ኃጢ
አትን ያርቃል" ። ማቴ ፳፫ ፡ ፴፱ ። ኢሳ ፳፯ ፡
፱ ። ፶፱ ፡ ፳ ። መዝ ፲፬ ፡ ፯ ።
ኃጢአታቸውን ባራቅሁላቸው ጊዜ በእሱ ተስፋቸ ፳፯
ውን ያገኛሉ ። ኤር ፴፩ ፡ ፴፩ - ፴፬ ።
በወንጌል በኩል ስለእናንተ ጠላቶቻችን ናቸው ፡ ፳፰
አባቶቻችን የተመረጡ በመሆናቸው ግን ወንድሞ
ቻችን ናችሁ ።
በእግዚአብሔር ጸጋ ጸጸት የለምና ። ፳፱
ቀድሞ እናንተ እግዚአብሔርን እንደካዳችሁት ዛሬ ፴
ግን ይቅር ብሏችኋል ።
እንዲሁም እነሱ ፡ ይቅር ይላቸው ዘንድ ዛሬ ካዱት ። ፴፩

እግዚአብሔር ሁሉን ይቅር ይለው ዘንድ ሁሉን በኃ ፴፪
ጢአት በረት ዘግቶታልና ። ገላ ፫ ፡ ፳፪ ። ፩ ጢሞ
፪ ፡ ፬ ።

፴፫ ኦ ዕመቂሁ ለብዕለ ጥበቢሁ ወአእምሮቱ ለእግዚአብ
ሔር ወእልቦ አሠር ለፍኖቱ ወአልቦ ዘየአምሮ
ለፍትሑ ።

፴፬ ወመኑ የአምር ሕሊናሁ ለእግዚአብሔር ወመኑ
ተማከሮ ።

፴፭ ወመኑ ለቅሐ ወተፈድዮ ።
፴፮ እስመ ኵሉ እምኔሁ ወኵሉ በእንቲአሁ ወኵሉ ቦቱ
ወሎቱ ስብሐት ለዓለመ ዓለም ፡ አሜን ።

## ምዕራፍ ፲ወ፪ ።

### ክፍል ፱ ፡ ምክር ከመ ንረሲ ነፍስተነ መሥዋዕተ ቅዱሰ ።

፩ አስተበቍዐክሙ አኀዊነ በሣህሉ ለእግዚአብሔር
ረስዩ ነፍስተክሙ መሥዋዕተ ቅዱሰ ለእግዚአብሔር
ወሕያወ ወሥሙረ ወኀሩየ ይኩን ቍርባንክሙ ወቀ
ኖክሙ ነበቢ ።

፪ ኢታፍቅርዎ ለዝ ዓለም ወሐድሱ ልበክሙ ወአመ
ክሩ ዘይፈቅድ እግዚአብሔር ዘሠናይ ወዘጽድቅ
ወዘፍጹም ።

፫ ወእነግረክሙ ለኵልክሙ በጸጋ እግዚአብሔር ዘተ
ውህበ ሊተ ከመ ኢትትዓበዩ ወኢተሐልዩ ትዝኅ
ርተ ፡ አላ ሐልዩ በዘታነጽሑ ርእሰክሙ እምዝሙት
ወኵሉ በከመ ከፈሎ እግዚአብሔር በመሥፈርተ
ሃይማኖቱ ።
፬ በከመ በውስተ አሐዱ ነፍስትነ ብዙኅ መለያልይ ብነ
ወዘዘዚአሁ ምግባሩ ።
፭ ከማሁ ኵልነ እንዘ ብዙኃን አሐዱ ሥጋ ንሕነ
በክርስቶስ ።
፮ ወብክሙ ጸጋ እግዚአብሔር ወዘዘዚአሁ ጸጋሁ ዘሂ
ይትኔበይ በሐሳበ ሃይማኖቱ ።

፯ ወዘሂ ይትለአክ በመልእክቱ ወዘሂ ይሜህር በት
ምህርቱ ።
፰ ወዘሂ ይትፌሣሕ በፍሥሐሁ ፡ ወዘሂ ይሠየም ከመ
ያሥልጥ መልእክቶ ወዘሂ ይምሕር በምሕረቱ ።

### ክፍል ፱ወ፩ ፡ በእንተ ምግባረ ሠናይ ዘዘዚአሁ ።

፱ ተፋቀሩ ዘእንበለ ኑፋቄ ተገኀሡ እምእኩይ ወት
ልዉ ሠናየ ።
፲ ወአድልዉ ለጽድቅ አፍቅሩ ቢጸክሙ ወኩኑ
መሐርያነ ።

የእግዚአብሔር የዕውቀቱ ፣ የጥበቡ ስፋት አወይ ፴፫
ጥልቅነቱ! ለመንገዱም ፍለጋ የለውም ፣ ፍርዱንም
የሚያውቀው የለም ። ምዕ ፱ ፡ ፳፫ ። ፲ ፡ ፲፪ ። ኢሳ
፵፭ ፡ ፲፭ ።
የእግዚአብሔርን ሐሳብ ማን ያውቃል ? ማንስ ተማ ፴፬
ከረው ? ። ኢዮብ ፲፭ ፡ ፰ ። ኢሳ ፵ ፡ ፲፫ ። ኤር ፳፫ ፡
፲፰ ። ፩ ቆሮ ፪ ፡ ፲፮ ።
ማን አበደረው ? ማንስ ብድር ከፈለው ። ኢዮ ፴፭ ፡ ፯ ። ፴፭
ሁሉ ከሱ ነውና ሁሉም እሱን ለማገልገል ተፈጥሮ ፴፮
አልና ሁሉም በእሱ ሥልጣን ተገኝቷልና ክብር
ምስጋና ለርሱ ይሁን ፣ ለዘለዓለሙ አሜን ።

## ምዕራፍ ፲፪ ፤

### ክፍል ፱ ፡ ሰውነታችንን የተቀደሰ መሥዋዕት እንድናደርግ የተሰጠ ምክር ።

ወንድሞቼ! በእግዚአብሔር ቸርነት እማልዳችኋለሁ ፩
ሰውነታችሁን ለእግዚአብሔር የተቀደሰ መሥዋዕት
አድርጉ ቍርባናችሁም ሕያው የተወደደና የተመ
ረጠ ይሁን ፣ አገልግሎታችሁም ሥራችሁን የሚመ
ሰክር ይሁን ። ምዕ ፮ ፡ ፲፫ ። ፩ ጴጥ ፪ ፡ ፭ ።
ይህን ዓለም አትውደዱት ፣ አእምሮአችሁን አድሱ ፣ ፪
እግዚአብሔር የሚወደውን መልካምና እውነት የሆ
ነውን ጉድለት የሌለበትን ዕወቁ ። ኤፌ ፬ ፡ ፳፫ ።
፭ ፡ ፲ · ፲፯ ።
በተሰጠኝ በእግዚአብሔር ጸጋ ሁላችሁም እንዳትታ ፫
በዩ እነግራችኋለሁ ፡ ኵራትን አታስቡ ራሳችሁን
ዝሙትን ከመሻት የምታነጹበትን አስቡ እንጂ ፣
ሁሉም እንደ ሃይማኖቱ መጠን እግዚአብሔር እንደ
አደለው ሆኖ ይኑር ። ፩ ቆሮ ፲፪ ፡ ፲፩ ። ኤፌ ፬ ፡ ፯ ።
በአንዱ ሰውነታችን ብዙ አካል ብልት እንዳለ ፡ ፬
ሥራውም ልዩ ልዩ እንደሆነ ። ኤፌ ፬ ፡ ፳፭ ።
እንዲሁ ሁላችን ብዙዎች ስንሆን በክርስቶስ አንድ ፭
አካል ነን ። ፩ ቆሮ ፲፪ ፡ ፳፯ ።
ከእግዚአብሔር የተሰጣችሁ ጸጋ አላችሁ ጸጋውም ፮
ልዩ ልዩ ነው ፣ ትንቢት የሚናገር እንደ ሃይማኖቱ
መጠን ። ፩ ቆሮ ፲፪ ፡ ፬ ።
የሚያገለግልም በማገልገሉ ይፅና የሚያስተምርም ፯
በማስተማር ይትጋ ። ፩ ጴጥ ፬ ፡ ፲ - ፲፩ ።
የሚሰጥም ደስ ብሎት ይስጥ ፣ የተሾመውም በማስ ፰
ተዋል ግዳጁን ይፈጽም ፣ የሚመጸውትም ደስ ብሎት
ይመጽውት ። ማቴ ፮ ፡ ፫ ። ፪ ቆሮ ፰ ፡ ፪ ፫ ።

### ክፍል ፱፩ ፡ ስለ ልዩ ልዩ በጎ ምግባር ።

ያለ መጠራጠር ተዋደዱ ፣ ከክፉ ርቃችሁ በጎውን ፱
ያዙ ። አሞ ፭ ፡ ፲፭ ። ፩ ጢሞ ፩ ፡ ፭ ። መዝ ፺፯ ፡ ፲ ።
ለእውነት አድሉ ፡ ባልንጀራችሁን ውደዱ ፣ ርኅሩኀን ፲
ሁኑ ። ፊል ፪ ፡ ፫ ።

፲፩ ተካበሩ በበይናቲክሙ ወአክብሩ መኳንንቲክሙ ።

፲፪ ወለጻሕቅ ኢትትሀከዩ ፡ ለመንፈስ ተሐይዉ ለእግዚ
አብሔር ተቀነዩ ፡ ለተስፋክሙ ተፈሥሑ ፡ ለሕማ
ምክሙ ተዐገሡ ፡ ለጸሎትክሙ ተጸመዱ ።
፲፫ ለግብረ ቅዱሳን ተሳተፉ ፡ አፍቅሮ ነግድ አትልዉ ።

፲፬ ደኀርዎሙ ለእለ ይሰድዱክሙ ፡ ደኀሩ ወኢ
ትርግሙ ።

፲፭ ምስለ ዘይትፌሣሕ ተፈሥሑ ፡ ወምስለ ዘይበኪ
ብክዩ ።

ክፍል ፺ወ፪ ፡ በእንተ ሕሊና ሠናይ ።

፲፮ ወከመዝ ሐልዩ ምስለ ቢጽክሙ ወትዕቢተሰ ኢተ
ሐልዩ ወከመ ዘያቴሕት ርእሶ ተመሰሉ ።
፲፯ ወኢትበሉ ጠቢባን ንሕነ ወኢትፍድይዎ እኩየ ለዘ
አሕሰመ ለክሙ ፡ ሠናየ ተናገሩ ምስለ ቢጽክሙ ።

፲፰ ወእመሰ ይትከሀለክሙ ምስለ ኵሉ ሰብእ ተአኀዉ ።

፲፱ ወኢትትበቀሉ ለሊክሙ ፡ አኀዊነ አኀልፍዋ ለመዓት
እስመ ከመዝ ይቤ አነ እትቤቀል ወአነ እትፈደይ
ይቤ እግዚአብሔር ።
፳ ወእመኒ ርኅበ ጸላኢከ አብልዮ ፡ ወለእመኒ ጸምአ
አስትዮ ወዘንተ ለእመ ገበርከ አፍሐመ እሳት ታስ
ተጋብእ ዲበ ርእሱ ።
፳፩ ወኢትማዕ ለእኩይ በእኩይ አላ ማዕ ለእኩይ በገ
ቢረ ሠናይ ።

ምዕራፍ ፲ወ፫ ።

ክፍል ፺ወ፫ ፡ በእንተ ተኰንኖ ለመኳንንት ።

፩ ለኵሉ ነፍስ መኰንን ተኰነኑ እስመ ኢይሠየም
መኰንን ዘእንበለ እምኀበ እግዚአብሔር ውእቱ
ኵሉ ብዉሕ ሎቱ ።
፪ ወዘሰ አበየ ተኰንኖ ለመኰንን ትእዛዘ እግዚአብ
ሔር አበየ ፡ ወአለሰ አበዩ ተኰንኖ ኵነኔ ያመጽኡ
ለርእሶሙ ።
፫ ወመኳንንትሰ ኢኮኑ ግሩማነ ለዘይገብር ሠናየ ዘእን
በለ ለዘእኩይ ምግባሩ ፡ ወእመሰ ትፈቅድ ኢትፍር
ሆሙ ለመኳንንት ግበር ሠናየ ወዓዲ እሙንቱ የአ
ኵቱከ እስመ ላእካነ እግዚአብሔር እሙንቱ ከመ
አንተ ታሠኒ ምግባረከ ።

፬ ወእመሰ ፈቀድከ ኢትፍራህ ግበር ሠናየ ወአኮ ለከ
ንቱ ዘእኰነንዎሙ መጥባሕተ አላ እስመ ላእካኑ
እሙንቱ ከመ ይትበቀልዎ ለገባሬ እኪት ።



እርስ በርሳችሁ ተከባበሩ ፡ መምህሮቻችሁንም አክ ፲፩
ብሩ ። ራእ ዮሐ ፫ ፡ ፲፭ ። ኤፌ ፭ ፡ ፲፯ ።
ከመትጋት አትስነፉ ፡ በማስተዋል ኑሩ ፡ ለእግዚአብ ፲፪
ሔር ተገዙ ፡ በተስፋችሁ ደስ ይበላችሁ መከራች
ሁን ታገሡ ለጸሎት ጽሙዳን ሁኑ ። ፩ ተሰ ፭ ፡ ፲፯ ።
እንግዳ መውደድን ጨምራችሁ ድኾችን ለመርዳት ፲፫
ተባበሩ ። ዘፍ ፲፰ ፡ ፫ ። ፲፱ ፡ ፪ - ፫ ። ዕብ ፲፫ ፡ ፪ ።
የሚያሳድዱአችሁን መርቁአቸው ፡ መርቁ እንጂ ፲፬
አትራገሙ ። ማቴ ፭ ፡ ፵፬ ። ግብ ሐዋ ፯ ፡ ፶፱ ። ፩
ቆሮ ፬ ፡ ፲፪ ።
ደስ ከሚለው ጋር ደስ ይበላችሁ ፡ ከሚያዝነውም ፲፭
ጋር እዘኑ ። መዝ ፴፭ ፡ ፲፫ ። ማቴ ፳፭ ፡ ፴፯ ።

ክፍል ፺፪ ፡ ስለ በጎ አስተሳሰብ ።

ለባልንጀራችሁ እንዲህ አስቡ ፡ ትዕቢትን ግን አታ ፲፮
ስቡ ራሱን የሚያዋርደውን ሰው ምሰሉ ። ምዕ ፲፭ ፡ ፭ ።
እኛ አዋቆች ነን አትበሉ ፡ ክፉ ላደረገባችሁ ክፉ ፲፯
አትመልሱለት ፡ ከባልንጀሮቻችሁ ጋር በጎ በጎውን
ተነጋገሩ ። ኢሳ ፭ ፡ ፳፩ ። ፩ ተሰ ፭ ፡ ፲፭ - ፳፬ ።
የሚቻላችሁስ ቢሆን ከሰው ሁሉ ጋር ወንድሚ ወን ፲፰
ድሚ ተባበሉ ። ማር ፱ ፡ ፶ ። ዕብ ፲፪ ፡ ፲፬ ።
ወንድሞቻችን አትበቀሉ ፡ ቍጣን አርቁት "እግዚአ ፲፱
ብሔር እኔ እበቀላለሁ እኔ ብድር እመልሳለሁ ይላል"
ብሏልና ። ዘሌ ፲፱ ፡ ፲፰ ። ዘዳ ፴፪ ፡ ፴፭ ። ማቴ ፭ ፡ ፴፱ ።
ጠላትህ ቢራብ አብላው ፡ ቢጠማም አጠጣው ፡ ይህን ፳
ብታደርግ የእሳት ፍሕም በራሱ ላይ ትሰበስባለህ ።
ምሳሌ ፳፭ ፡ ፳፩ - ፳፪ ። ማቴ ፭ ፡ ፵፬ ።
ክፉውን በክፉ ድል እነሳዋለሁ አትበል ፡ ክፉውን ፳፩
በበጎ ሥራ ድል ንሳው እንጂ ።

ምዕራፍ ፲፫ ፤

ክፍል ፺፫ ፡ ሥልጣን ላላቸው ስለ መገዛት ።

ለተሾመ ሁሉ ተገዙ ፡ ያለ እግዚአብሔር ፈቃድ ገዢ ፩
አይሾምምና ሙሉ ሥልጣን አለው ። ዳን ፬ ፡ ፳፱ - ፴ ።
ቲቶ ፫ ፡ ፩ ። ዮሐ ፲፱ ፡ ፲፩ ። ምሳ ፰ ፡ ፲፭ ።
ለተሾመው አልገዛም ያለ የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ፪
እምቢ አለ ፡ መገዛትን እምቢ የሚሉ ለራሳቸው ቅጣ
ትን ያመጣሉ ።
መኳንንትስ ሥራው ክፉ ለሆነ እንጂ መልካም ለሚ ፫
ሠራስ የሚያስፈሩ አይደሉም ፡ መኳንንትን ላትፈራ
ቸው ብትፈልግ መልካም አድርግ እነሱም ደግሞ
ያከብሩሃል አንተ ሥራህን ታሳምር ዘንድ ፡ የእግዚአ
ብሔር መልእክተኞች ናቸውና ። ፪ ሳሙ ፳፫ ፡ ፫ ።
፩ ጴጥ ፪ ፡ ፲፫ - ፲፬ ።
እንዳትፈራ ከወደድህ መልካም አድርግ ፡ ሥልጣን ፬
የሰጧቸው ለከንቱ አይደለምና ክፉ አድራጊውን
ሊበቀሉ መልእክተኞቹ ናቸው እንጂ ። መዝ ፹፪ ፡ ፯ ።

፭ ወይእዜኒ በግብር ተኰነኑ ወአኮ ዳእሙ ለዘእኩይ ምግባሩ ዓዲ ለዘሠናይኒ ምግባሩ ።

፮ ወበእንተዝ ታገብኡ ሎሙ ጸባሕተ እስመ ላእካነ እግዚአብሔር እሙንቱ ወለዝ ግብር ተሠይሙ ።

፯ ወለኵሉ በዘይረትዕ ግበሩ ወለዘሂ ጸባሕተ ጸብሑ ወለዘሂ ብነተ በንቱ ወለዘሂ ዓሥራተ ዓሥሩ ወለዘሂ ፍርሃተ ፍርሁ ወለዘሂ ክብረ አክብሩ ።

## ክፍል ፶ወ፬ ፡ በእንተ አፍቅሮ ቢጽ ።

፰ ወአልቦ ዘይበቍዓክሙ ዘእንበለ አፍቅሮ ቢጽክሙ ወዘሰ አፍቀረ ቢጾ ኵሎ ሕገ ፈጸመ ገቢረ ።

፱ እስመ ከመዝ ይቤ በኦሪት ኢትሑር ብእሲተ ብእሲ ወኢትቅትል ነፍሰ ፡ ወኢትስርቅ ወኢትኩን ስምዐ በሐሰት ወኢትፍቱ ወዓዲ ባዕድኒ ቦቱ ትእዛዝ ወር እሱ ለኵሉ አፍቅር ቢጸከ ከመ ነፍስከ ።

፲ ዘያፈቅር ቢጾ ኢይገብር እኩየ ፡ ተፋቅሮሰ ፍጹም ሕግ ውእቱ ።

## ክፍል ፶ወ፭ ። በእንተ ሕይወት ።

፲፩ ወዘኒ ተአምሩ ከመ በጽሐ ጊዜሁ ለነቂሕ እምንዋም ፡ ወይእዜሰ አልጸቀት ሕይወትነ እንተ ተሰፈውናሃ ።

፲፪ ኀለፈት ሌሊት ወመጽአት መዓልት ወንግድፍ እምላዕሌነ ምግባረ ጽልመት ወንልበስ ወልታ ብርሃን ።

፲፫ በምግባረ ጽድቅ ወአኮ በተውኔት ወበማኅሌት ወበስታይ ወበዝሙት ወበምርዓት ወአኮ በተሐምሞ ወበቅንአት ።

፲፬ ልበስዎ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወኢተሐልዩ ፍትወተ ሥጋክሙ ።

## ምዕራፍ ፲ወ፬ ።

## ክፍል ፶ወ፮ ፡ በእንተ ዘድኩም ሃይማኖቱ ።

፩ ወለዘኒ ድኩም ሃይማኖቱ ፁርዎ ወአጽንዕዎ ወኢትግበሩ ለአድልዎ ።

፪ ዘሰ የአምን ከመ ኵሉ ብውሕ ሎቱ ኵሎ ለይብላዕ ወዘሰ ይናፍቅ ሐምለ ለይሴሰይ ።

፫ ወዘኒ ይበልዕ ኢይመንኖ ለዘኢይበልዕ ወዘኒ ኢይበልዕ ኢይግእዞ ለዘይበልዕ ፡ እስመ ለኵሎሙ እግዚአብሔር አእመሮሙ ።

፬ ምንትኑ አንተ ዘትግእዝ ነባሬ ባዕድ እንዘ ለእግዚኡ



አሁንም በግድ ተገዙ ግን ሥራው ክፉ ለሆነ ብቻ አይደለም ሥራው መልካም ለሆነውም ነው እንጂ ። መክ ፰ ፡ ፪ ። ፩ ጴጥ ፪ ፡ ፲፫ ። ፭

ስለዚህም ግብር ታገቡላቸዋላችሁ የእግዚአብሔር መልእክተኞች ናቸውና ለዚሁ ሥራም ተሹመዋልና። ፮

ለሁሉም እንደሚገባው አድርጉ ፡ ግብር ለሚገባው ግብር ስጡ ፡ እንቍጣጣሽ ለሚገባው እንቍጣጣሽ ስጡ ፡ መፈራት የሚገባውን ፍሩ ፡ መክበር የሚገባውን አክብሩ ። ማቴ ፳፪ ፡ ፳፩ ። ማር ፲፪ ፡ ፲፯ ። ፯

## ክፍል ፶፬ ፡ ወንድምን ስለ መውደድ ።

ባልንጀራችሁን ከመውደድ በቀር የሚጠቅማችሁ ነገር የለም ፡ ባልንጀራውን የወደደ ግን ሕግን ሁሉ ሠርቶ ፈጸመ ። ዘሌ ፲፱ ፡ ፫ ። ምሳ ፳፬ ፡ ፳፩ ። ፰

በኦሪት "ወደ ጕልማሳ ሚስት አትሂድ ፡ ነፍስ አትግደል ፡ አትስረቅ ፡ በሐሰት ምስክር አትሁን ፡ አትመኝ ፡ ብዒልና ሌላም ትእዛዝ አለው ፡ ግን የሁሉም መጨረሻው ባልንጀራህን እንደራስህ ውደድ„ ነው ። ዘሌ ፲፱ ፡ ፲፰ ። ፱

ባልንጀራውን የሚወድ ክፉ አይሠራም ፡ ፍቅርስ ፍጹም ሕግ ነው ። ማቴ ፳፪ ፡ ፵ ። ፩ ቆሮ ፲፫ ፡ ፬ ። ፲

## ክፍል ፶፭ ፡ ስለ ሕይወት ።

ይህንንም ታውቃላችሁ ከእንቅልፍ ለመንቃት ጊዜው እንደ ደረሰ ፡ አሁንማ ተስፋ አድርገናት የነበረችው ሕይወታችን ደረሰች ። ኤፌ ፭ ፡ ፲፬ ። ፩ ተሰ ፭ ፡ ፮ - ፯ ። ዕብ ፯ ፡ ፱ ። ፲፩

ሌሊት አለፈች ፡ ቀን መጣች ፡ የጨለማን ሥራ ከኛ እናርቅ የብርሃንንም ጋሻ እንልበስ ። ፩ ዮሐ ፪ ፡ ፰ ። ፲፪

በውነት ሥራ ጸንተን እንኑር ፡ በጨዋታ ፡ በዘፈን ፡ በስካር ፡ በዝሙት ፡ በመዳራት አይደለም ፡ በቅናትና በምቀኝነትም አይደለም ። ሉቃ ፳፩ ፡ ፴፬ ። ፲፫

ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስን ምሰሉት ፡ የሥጋችሁን ፍላጎት አታስቡ ። ገላ ፫ ፡ ፳፯ ። ፲፬

## ምዕራፍ ፲፬ ፤

## ክፍል ፶፮ ፡ ሃይማኖቱ ደካማ ስለ ሆነ ሰው።

ሃይማኖቱ ደካማ የሆነውን ሰው ታገሡት አጽናኑት በግብዝነት አትሥሩ ። ኢሳ ፵፭ ፡ ፫ - ፬ ። ምዕ ፲፭ ፡ ፩ ። ፩ ቆሮ ፰ ፡ ፱ ። ፩

ሁሉ እንደ ተፈቀደለት የሚያምን ሁሉን ይብላ ፡ የሚጠራጠር ግን አህልን ተክልን ይብላ ። ዘፍ ፩ ፡ ፳፱ ። ፩ ቆሮ ፲ ፡ ፳፭ ። ፪

የሚበላውም የማይበላውን አይንቀፈው ፡ የማይበላም የሚበላውን አይጸየፈው ፡ ለሁሉም እግዚአብሔር አውቆላቸዋልና ። ቈላ ፪ ፡ ፲፮ ። ፫

አገልግሎቱ ለጌታው ሲሆን የሌላውን አገልጋይ የም ፬

ይቀውም እመኒ ወድቀ ለእግዚኡ ይቀውም ወይ
ክል እግዚአብሔር አቅሞቶ ።

፭ እስመ ቦ ዘይትሔረም እምዕለት ዕለተ ወቦ ዘይትሔ
ረም በኵሉ መዋዕል ወባሕቱ ለኵሉ በከመ አዘዘ
ልቡ ።

፮ ዘኒ ተሐረመ በበዕለቱ ለእግዚአብሔር ተሐረመ ፡
ወዘኒ ተሐረመ በኵሉ መዋዕል ለእግዚአብሔር
ተሐረመ ፡ ወዘኒ በልዐ ለእግዚአብሔር በልዐ ወየአ
ኵቶ ለእግዚአብሔር ፡ ወዘኒ ኢበልዐ ለእግዚአብ
ሔር ኢበልዐ ወየአኵቶ ለእግዚአብሔር ።

ክፍል ፶ወ፯ ፡ በእንተ ሐይው ለእግዚአብሔር ።

፯ ወአልቦ እምውስቴትነ ዘለርእሱ የሐዩ ወዘለርእሱ
ይመውት ።

፰ ወእመኒ ሐየውነ ለእግዚአብሔር ነሐዩ ፡ ወእመኒ
ሞትነ ለእግዚአብሔር ንሕነ ።

፱ ወበእንተዝ ሞተ ክርስቶስ ወሐይወ ከመ ይኩንን
ሕያዋነ ወሙታነ ።

፲ ምንትኑ አንተ እንከ ዘትግእዝ ቢጸከ ወምንትኑ አንተ
ዘትሚንን ቢጸከ እንዘ ሀለወነ ኵልነ ንብጻሕ ቅድመ
መንበረ ምኵናኑ ለክርስቶስ ።

፲፩ እስመ ከመዝ ይቤ እግዚአብሔር ሕያው አነ እስመ
ሊተ ይሰግድ ኵሉ ብርክ ወሊተ ይገኒ ኵሉ ልሳን ።

፲፪ ናሁ ተዓውቀ ከመ ሀለወነ ኵልነ ንትሐተት በኀበ
እግዚአብሔር ።

፲፫ ወኢንግእዝ እንከ ቢጸነ ወዘንተ ዳእሙ ነሐሊ በዘኢ
ንግእዝ ቢጸነ ።

ክፍል ፶ወ፰ ፡ በእንተ ዘአልቦ ሙስና እንበይነ መብልዕ ።

፲፬ ወአአምር ወእትአመን በእግዚእነ ኢየሱስ ከመ
አልቦ ዘይማስን በእንቲአሁ ለሙሱን ዳእሙ ኵሉ
ይማስን ።

፲፭ ወእመሰ እንበይነ መብልዕ ተሐይሶ ለቢጽከ አልብከኬ
ተፋቅሮ በኑ እንበይነ መብልዕ ይትኀጐል ዝኩ ዘበእ
ቲአሁ ሞተ ክርስቶስ ።

፲፮ ኢትፅርፉ እንከ ሳዕለ ሠናይ ዘጸገወነ እግዚእነ ።

፲፯ እስመ ኢኮነ መንግሥተ እግዚአብሔር መብልዐ
ወመስቴ ዘእንበለ ጽድቅ ወሰላም ወፍሥሐ በመን
ፈስ ቅዱስ ።

፲፰ ወዘሰ ከመዝ ይትቀነይ ለክርስቶስ ሥሙር በኀበ እግ
ዚአብሔር ወኅሩይ በኀበ ሰብእ ።



ትነቅፍ አንተ ምንድነህ ? ቢወድቅም ጌታውን ለማ
ገልገል ይነሣል ፡ እግዚአብሔር ሊያስነሣው ይችላ
ልና ። ማቴ ፯ ፡ ፩ ። ያዕ ፬ ፡ ፲፩ - ፲፪ ።

አንዳንድ ዕለት የሚከለከል ፡ አለ ዘወትር የሚከለከ ፭
ልም አለና ፡ ነገር ግን ሁሉ ልቡ እንደ ወደደ ያድ
ርግ ። ገላ ፬ ፡ ፲ ።

አንዳንድ ጊዜ የተከለከለም ለእግዚአብሔር ብሎ ፮
ተከለከለ ፡ ዘወትር የተከለከለም ለእግዚአብሔር ብሎ
ተከለከለ ፡ የበላም እግዚአብሔርን ለማመስገን በላ ፡
እግዚአብሔርንም ያመሰግነዋል ፡ ያልበላም እግዚአ
ብሔርን ለማመስገን አልበላም ፡ እግዚአብሔርንም
ያመሰግነዋል ። ዘዳ ፳ ፡ ፲ ። ፩ ቆሮ ፲ ፡ ፴፩ ።

ክፍል ፶፯ ፡ እግዚአብሔርን ለማገልገል ስለ መኖር ።

ከመካከላችን ለራሱ ብሎ የሚኖር ለራሱ ብሎ የሚ ፯
ሞት የለም ።

ብንኖርም እግዚአብሔርን ለማገልገል እንኖራለን ፡ ብን ፰
ሞትም እግዚአብሔርን ለማገልገል እንሞታለን ብን
ኖርም ብንሞትም ለእግዚአብሔር ነን ። ገላ ፪ ፲ ።

ስለዚህም ክርስቶስ ሕያዋንን ሙታንን ይገዛ ዘንድ ፱
ሙቶ ተነሣ ። ግብ ሐዋ ፲ ፡ ፵፪ ።

እንግዲህ ወንድምህን የምትነቀፍ አንተ ምንድር ፲
ነህ ? ወንድምህን የምትንቅ አንተስ ምንድር ነህ ?
ሁላችን ክርስቶስ በሚፈርድበት ዙፋን ፊት የምን
ቆም ስንሆን ። ግብ ሐዋ ፲፯ ፡ ፴፩ ። ማቴ ፳፭ ፡ ፴፩-፴፪ ።

እግዚአብሔር እኔ ሕያው ነኝ ፡ ጕልበትም ሁሉ ለእኔ ፲፩
ይሰግዳል ፡ አንደበትም ሁሉ ለእኔ ይገዛል ብሏልና ።
ኢሳ ፵፭ ፡ ፳፫ ። ፊል ፪ ፡ ፲ ።

ሁላችንም በእግዚአብሔር ዘንድ እንደምንመረመር ፲፪
እነሆ ታወቀ ። ማቴ ፲፪ ፡ ፴፮ ።

እንግዲያስ ወንድማችንን አንነቀፍ ወንድማችንንም ፲፫
እንዳንነቅፍ ይህን ብቻ እናስብ ። ማቴ ፲፰ ፡ ፯ ።

ክፍል ፶፰ ፡ በመብል ጕዳት ስላለመኖሩ ።

በርሱ ስለማመኑ የሚጐዳ እንደሌለ ዐውቃለሁ ፡ ፲፬
በጌታችን በኢየሱስም አምናለሁ ፡ ለማያምን ግን
ሁሉ ርኩስ ነው ። ግብ ሐዋ ፲ ፡ ፲፭ ። ቲቶ ፩ ፡ ፲፭ ።

በመብል ምክንያት ወንድምህን የምትነቅፍ ከሆን ፲፭
ክስ ፍቅር የለህማ ! በውኑ ክርስቶስ ስለርሱ የሞተ
ለት ይህ በመብል ምክንያት ይጐዳልን ? ፩ ቆሮ ፰ ፡
፲፩ - ፲፫ ።

እንግዲህ ጌታ በሰጠን በበጎው ነገር አትሳደቡ ። ፲፮

የእግዚአብሔር መንግሥት በመብል በመጠጥ አይ ፲፯
ደለምና ፡ ሃይማኖት ፡ ፍቅር ፡ በመንፈስ ቅዱስ የሚ
ገኝ ደስታ ነው እንጂ ። ሉቃ ፲፯ ፡ ፳ ። ፩ ቆሮ ፰ ፡ ፰ ።

ለክርስቶስ እንዲህ የሚገዛ ግን በእግዚአብሔር ዘንድ ፲፰
የተወደደ ፡ በሰውም ዘንድ የተመረጠ ነው ።

| | ኀበ ሰብአ ቆሮንቶስ ፪ ። | ወደ ቆሮንቶስ ሰዎች ፪ ። | |
|---|---|---|---|
| ፭ | ወበተቀሥፎ ወበትሞቅሖ ወበሥራሕ ወበተሀውኮ በትጋሀ ወበጾም ። | በመገረፍ በመታሠር በመድከም በመታወክ በመትጋት በመጾም ። ምዕ ፲፩ ፳፫ - ፳፯ ። | ፭ |
| ፮ | በንጽሕ ወበአእምሮ በምክር ወበተዓግሦ በምሕረ ወበመንፈስ ቅዱስ በፍቅር ዘአንበለ አድልዎ ። | በንጽሕና ፣ በዕውቀት ፣ በምክር ፣ በመታገሥ ፣ በመራራት ፣ በንጹሕ ልብ ፣ ያለማድላት ፍቅር ። ፩ ጢሞ ፬ ፲፪ ። | ፮ |
| ፯ | በነገረ ጽድቅ ዘአንበለ ኑፋቄ በኃይለ እግዚአብሔር ወወልታ ጽድቅ ዘእምየማን ወዘእምጸጋም ። | ጥርጥር በሌለው ሃይማኖት በእግዚአብሔር ኃይል ከቀኝ ከግራ ከሚመጣው የጽድቅ ጋሻ የሚሆናችሁን የእግዚአብሔርን ኃይል ተደገፋችሁ ። ፩ ቆሮ ፪ ፬ ። | ፯ |
| ፰ | በክብር ወበኀሣር በምድኃር ወበመርገም ከመ ኃጥአን ወጻድቃን ። | ቢያከብሯችሁም ቢያዋርዷችሁም ቢመርቋችሁም ቢረግሟችሁም ኃጢአተኞች ቢያስመስሏችሁ እንደ ጻድቃንም ቢያደርጓችሁ ። | ፰ |
| ፱ | ከመ እለ ኢየአምርዎሙ ወዕዉቃን ከመ ዓብዳን ፣ ወጠቢባን ከመ ምውታን ፣ ሕያዋን ከመ ምንስዋን ፣ ወኢቅቱላን ከመ ነዳያን ። | እንደማያውቋቸው እንደሚያውቋቸውም ቢያደርጓችሁ እንደ ዐላዋቆች ፣ እንደ ዐዋቂዎች ቢያደርጓችሁ እንደ ሙታን እንደ ሕያዋን ቢቈጥሯችሁ ድል እንደ ተነሡ እንዳልተነሡ ቢያደርጓችሁ ። መዝ ፻፲፰ ፲፰ ። | ፱ |
| ፲ | ከመ ትኩዛን ወከመዒ ዘልፈ ትትፌሥሑ ከመ ነዳያን ወብዙኃነ ታብዕሉ ከመ ዘአልብክሙ ወኢምንተኒ ወኵሉ ውስተ እዴክሙ ። | እንደታምዝኑ ወይም ዘወትር ደስ እንደሚላችሁ ቢያደርጓችሁ ወይም እንደ ደኻያችሁ ብዙዎችን እንደ ምታበለጽጉ ምንም ምን እንደሌላችሁ ፣ ወይም ሁሉ እንዳለ ቢያደርጓችሁ በዚህ ሁሉ እግዚአብሔርን አገልግሉ ። | ፲ |
| ፲፩ | አፉነ ክሡት ለክሙ ኦ ሰብአ ቆሮንቶስ ወርኂብ ልብነ ። | የቆሮንቶስ ሰዎች! ለእናንተ አፋችን የተከፈተ ልባችንም የሰፋ ነው ። | ፲፩ |
| ፲፪ | ወአልብነ ንሂክ እምኔክሙ ወኢላዕሌክሙ እምኔነ አላ ንህክሙ ወተመንደብክሙ ለምሕረትክሙ ። | ከእናንተ የመጣ ኀዘን በኛ ላይ ፣ ከእኛም የመጣ ኃዘን በእናንተ ላይ የለም ፤ ይቅርታን ለመቀበል መከራ ተቀብላችሁ አዝናችኋል እንጂ ። ምዕ ፲፪ ፲፭ ። | ፲፪ |
| ፲፫ | እብለክሙ ከመ ዘለደቂቅየ በእንተ ውእቱ ፍድዩ ዘይደሉ ሊተ ላዕሌክሙ አርኅቡ ሊተ አፍቅሮተክሙ አንትሙኒ ። | ለልጆቼ እንደምናገር እነግራችኋለሁ ፣ ስለዚህ ከእናንተ ሊከፈለኝ የሚገባውን ክፈሉኝ እናንተም ፍቅራችሁን አብዙልኝ ። ፩ ቆሮ ፬ ፲፬ ። | ፲፫ |
| ፲፬ | ወኢትኩኑ ንፉቃነ ኢትሑሩ ውስተ አርዑተ እለ ኢየአምኑ መኑ ዘያስተዔርዮ ለጽድቅ ምስለ ኃጢአት ወመኑ ዘይዴምሮ ለብርሃን ምስለ ጽልመት ። | ተጠራጣሪዎች አትሁኑ ወደማያምኑ ሰዎች ማኅበር አትሂዱ ጽድቅን ከኃጢአት ጋር አንድ የሚያደርጋት ማን ነው? ብርሃንስ ከጨለማ ጋር የሚቀላቀለው ማነው? ዘፀአ ፴፬ ፲፯ ። ዘዳግ ፯ ፪ ። ኤፌ ፭ ፲፩ ። | ፲፬ |
| ፲፭ | ወመኑ ዘያኀብሮ ለክርስቶስ ምስለ ቤልሆር ፣ ወመኑ ዘይከፍሎሙ ለመሃይምናን ምስለ ንፉቃን ። | ክርስቶስን ከሰይጣን ጋር አንድ የሚያደርገው ማነው? ምእመናንንስ ከመናፍቃን ጋር አንድ ወገን የሚያደርጋቸው ማነው? ። | ፲፭ |
| ፲፮ | ወመኑ ዘይዴምር ታቦተ እግዚአብሔር ውስተ ቤተ ጣዖት ፣ አኮኑ ንሕነ ውእቱ ቤቱ ለእግዚአብሔር ሕያው ፣ በከመ ይቤ እግዚአብሔር እነ አኀድር ኀቤሆሙ ወአንሶሱ ማእከሎሙ ወእከውኖሙ አምላኮሙ ወእሙንቱኒ ይከውኑኒ ሕዝብየ ። | የእግዚአብሔርንስ ታቦት በጣዖት ቤት ውስጥ የሚያኖር ማነው? የሕያው እግዚአብሔር ማደሪያዎች እኛ አይደለንምን? ፣ እግዚአብሔር "እኔ በነርሱ አድራለሁ በመካከላቸው እኖራለሁ ፣ አምላካቸውም እሆናቸዋለሁ" ፣ እነሱም ሕዝቤ ይሆኑኛል እንዳለ ። ዘሌ ፳፮ ፲፪ ። ፩ ቆሮ ፫ ፲፯ ። | ፲፮ |
| ፲፯ | ወበእንተ ዝንቱ ፃኡ እማእከሎሙ ወተፈለጡ ይቤ እግዚአብሔር ፣ ወኢትቅረቡ ኀበ ርኩሳን ወአነ እትዌከፈክሙ ። | ስለዚህ እግዚአብሔር ከመካከላቸው ተለይታችሁ ውጡ ወደ ርኩሳንም አትቅረቡ እኔም በረድኤት እቀበላችኋለሁ አለ ። ኢሳ ፶፫ ፳ ፤ ፶፪ ፲፩ ። | ፲፯ |
| ፲፰ | ወእከውነክሙ አበክሙ ወአንትሙኒ ትከውኑኒ ደቂቀየ ወአዋልድየ ይቤ እግዚአብሔር ዘኵሎ ይመልክ ። | ሁሉን የሚገዛ እግዚአብሔር አባት እሆናችኋለሁ እናንተም ወንዶች ልጆች ፣ ሴቶች ልጆች ትሆኑኛላችሁ አለ ። ኤር ፴፩ ፱ ። | ፲፰ |

ምዕራፍ ፯ ።

ክፍል ፱ ፡ በእንተ ዘከመ ይደሉ ተወክፎ አርዳእ ።

፩ ወበእንተ ዘብነ ተስፋ አኀዊነ ናንጽሕ ርእሰነ ወኢና
ግምን ነፍስተነ ወንግበር በዘንትቄደስ በፈሪሃ እግዚ
አብሔር ።

፪ ወይእዜኒ ተአምሩ አኀዊነ ከመ አልቦ ዘአማሰነ ወአ
ልቦ ዘገፋዕነ ወአልቦ ዘተዐገልነ ።

፫ ወአኮ ለአድልዎ ዘእብል እስመ ወዳእኩሂ እቤ ከመ
ምሉእን አንትሙ ውስተ ልብነ ለመዊትኒ ወለሐይ
ወትኒ ።

፬ ወከመዝ ብየ ብዙኀ ሞገስ በኀቤክሙ ወብዙኀ ትም
ክሕትየ በእንቲአክሙ ወፈጸምኩ ፍሥሐየ ወፈድ
ፈደኒ ኃሤትየኒ እምኵሉ ሕማምየ ።

፭ ወበጺሐነ መቄዶንያ ኢረከብነ ወኢአሐተኒ ዕረፍተ
ለነፍስነ ወበኵሉ አሕመሙነ በአፍአኒ ቀትል ወመን
ንሱት ፡ ወበውስጥኒ ፍርሃት ።

፮ ወባሕቱ ውእቱ እግዚአብሔር ዘያስተፌሥሖሙ
ለሕሙማን አስተፍሥሐነ በምጽአቱ ለቲቶ ።

፯ ወአኮ በምጽአቱ ባሕቲቱ ዓዲ በፍሥሐ ዘአስተፍ
ሣሕክምዎ ወዜነወነ አፍቅሮተክሙ ዘከመ ትጽሕቁ
ለነ ወትትቃሐዉ ፡ ወሰሚዐየ ዘንተ ጸንዐ ፍሥሐየ
ብክሙ ።

፰ ወእመኒ አተከዝኩክሙ ቀዳሚ በመጽሐፍ ዘጸሐ
ፍኩ ለክሙ ኢያኔስሐኒ ፡ ወእመኒ ነሳሕኩ ናሁ እሬ
እያ ለይእቲ መልእክት እመሂ ለአሐቲ ሰዓት አተከ
ዝኩክሙ ናሁ ይእዜ እትፌሣሕ በእንቲአሃ ብዙኀ ።

፱ ወአኮሰ ውእቱ እስመ ተከዝክሙ ዳእሙ እስመ ተከ
ዝክሙ ከመ ትነሥሑ እስመ እንበይነ እግዚአብሔር
ተከዝክሙ ከመ ኢይትኀጐል አሐዱሂ እምኔክሙ።

፲ እስመ ዘበእንተ እግዚአብሔር ኀዘን ንስሓሁ ለሕይ
ወት ዘለዓለም ይከውን ፡ ወትካዝሰ ዘበእንተ ዓለም
ሞተ ያመጽእ ።

፲፩ ወናሁ ውእቱ ትካዝ ዘበእንተ እግዚአብሔር ጻሕቀ
ወቅስተ ወፍርሀተ ወግርማ ወተፋቅሮ ወተቃሕዎ
ፍዳ ገብረ ለክሙ እስከ አቀምክሙ ርእሰክሙ በን
ጽሕ ወበምግባር ከመ ዘኢተአምሩ ወኢምንተኒ ።

፲፪ ወዘኒ ዘጸሐፍኩ ለክሙ አኮ በእንተ ዘገፍዐ ወዘተገ
ፍዐ ዳእሙ ከመ ይትዐወቅ ከመ ጽሕቀሙ በእንቲ
አነ በቅድመ እግዚአብሔር ።

፲፫ ወበእንተዝ ተፈሣሕነ ወዓዲ ዲበ ፍሥሐነ ተፈሣሕነ

ምዕራፍ ፯ ።

ክፍል ፰ ፡ ደቀ መዛሙርትን ስለ መቀበል ።

ወንድሞቻችን ! ይህ ተስፋ ያለን ስለሆነ ራሳችንን ፩
እናንፃ ፡ ሰውነታችንን በኃጢአት አናሳድፍ እግዚአ
ብሔርን በመፍራት የምንከብርበትን ሥራ እንሥራ ።
፩ ዮሐ ፫ ፫ ።
አሁንም ወንድሞቻችን! የበደልነው የገፋነውም ያጠ ፪
ፋነውም የቀማነውም እንደሌለ ታውቃላችሁ ። ግብ
ሐዋ ፳ ፴፫ ።
ለሰው ይምሰል የምናገር አይደለም ለሞትም ለሕይወ ፫
ትም ቢሆን እናንተ በልባችን እንዳላችሁ ፈጽሜ
ተናግሬአለሁና ። ምዕ ፯ ፲፩ - ፲፫ ።
በእናንተ ዘንድ እንዲህ ብዙ መወደድ አለኝ ፡ ስለ ፬
እናንተም የምመካበት ብዙ ነው ደስታዬን ፈጸ
ምኩ ደስታዬ ከመከራዬ ሁሉ ይልቅ በዝቶልኛ
ልና ። ፩ ቆሮ ፩ ፬ ። ፊል ፪ ፲፯ ።
ወደ መቄዶንያ በደረስንም ጊዜ ለሰውነታችን ፭
ጥቂት ስንኳ ዕረፍት አላገኘንም ፡ በሁሉ መከራ
አፀኑብን በውጭም ጠብ መጋደል ፡ በውስጥም
ፍርሃት መጨነቅ ነበር ።
ግን ያዘኑትን ደስ የሚያሰኝ እርሱ እግዚአብሔር ፮
በቲቶ መምጣት ደስ አሰኘን ። ዘዳግ ፴፪ ፴፭ ።
በመምጣቱም ብቻ አይደለም ፡ ደስ ባሰኛችሁት ደስ ፯
ታም ነው እንጂ ፡ ለእኛ እንደምትከራከሩና እንደም
ታስቡ ፍቅራችሁን ነግሮናልና ፡ ይህን ሰምቼ ደስታዬ
በእናንተ በዛ ።
መጀመሪያ በጻፍኩላችሁ ደብዳቤ ባሳዝናችሁም ፰
እንኳ አያፀፀተኝም ፡ ብፀፀትም እነሆ ያቺን መልእ
ክት አያታለሁ ፡ ለጥቂት ጊዜ ባሳዝናችሁም እነሆ
አሁን ስለ እርሷ በብዙ ደስ ይለኛል ። ምዕ ፪ ፬ ።
ደስታዬም ስለ አዘናችሁ አይደለም ንስሐ ል ፱
ገቡ ስለ አዘናችሁ ነው እንጂ ፡ ከእናንተ መካከል
አንዱ እንዳይጠፋ ስለ እግዚአብሔር አዝናችኋልና ።
ስለ እግዚአብሔር የሚደረግ ኀዘን ፀፀቱ ለዘለዓለም ፲
ሕይወት ይሆናልና ፡ ስለ ዓለም የሚደረግ ኀዘን ግን
ሞትን ያመጣል ። ፪ ሳሙ ፲፪ ፲፫ ። ኤር ፴፩ ፲፰-፳ ።
እነሆ ያ ስለ እግዚአብሔር ያደረጋችሁት ኀዘን ፲፩
ምንም ምን የማታውቁ እስከ መሆን ደርሳችሁ ራሳ
ችሁን በበጎ ሥራና በንጽሕ እስከታፀኑ ድረስ
ትጋትን መቃወምን መፈራራትን መከባበርን መዋ
ደድን መከራከርን ብድራት አደረገላችሁ ። ኤር ፵
፬ - ፭ ። ዘካ ፲፪ ፲ ።
ይህን የጻፍኩላችሁ ስለ በደለና ስለ ተበደለ አይደ ፲፪
ለም በእግዚአብሔር ፊት ስለእኛ እንደተጋችሁ
ይታወቅ ዘንድ ነው እንጂ ።
ስለዚህ ደስ አለን በደስታ ላይ ደስታን ጨመርን ፡ ይል ፲፫

ወፈድፋደስ በፍሥሓ ቲቶ እስመ አዕረፍክምዋ ለነ
ፍሱ በኀበ ኵልክሙ ።
፲፬ እስመ ኢያስተኀፈርክሙኒ በኵሉ ዘተመክሕኩ ሎቱ
በእንቲአክሙ አማነ ረሰይክሙ ለነ ዘነገርናክሙ ወከ
ማሁ እሙነ ኮነ ።
፲፭ ወፈድፋደ የአኵተክሙ ወይዜክረክሙ ዘከመ ትት
ኤዘዙ ሎቱ ወትትወከፍዎ በፍርሀት ወበረዓድ ።

፲፮ ወእትፌሣሕ ባሕቱ እስመ በኵሉ እትአመነክሙ ።

ምዕራፍ ፰ ።

<u>ክፍል ፲ ፡ በእንተ ዘከመ ይደሉ አስተዋጽኦ ።</u>

፩ ወእነግረክሙ አኀዊነ ጸጋ እግዚአብሔር ዘተውህበ
ለቤተ ክርስቲያን ዘመቄዶንያ ።

፪ እስመ እምብዙኀ መከራ ሕማሞሙ ፈድፋደ ፍሥሐ
ሆሙ ወምስለ ዕመቀ ንዴቶሙ ፈድፋደት ፍሥሓ
ብዕሎሙ ።
፫ እስመ ለልየ ሰማዕቶሙ ከመ በአምጣነ ኃይሎሙ
ወዘእንበለ ኃይሎሙሂ ጥቡዓን እሙንቱ ለሊሆሙ ።
፬ ወብዙኀ አስተብቍዑነ በእንተ ሱታፌ መልእክተ
ቅዱሳን ።
፭ ወአኮኒ በከመ ተሐዘብነ እስመ ለሊሆሙ አቅደሙ
በፈቃዶሙ ወመጠዉ ነፍሶሙ ለእግዚአብሔር ።

፮ ወአስተፍሥሐነ ቲቶ ወአስተብቋዕናሁ ከመ ይፈጽም
ለክሙ ጸጋሁ በከመ ወጠነ ።
፯ እስመ ፈድፋድክሙ በኵሉ በሃይማኖት ወበቃል
ወበጥበብ ወበጽሒቅ በኵሉ ዘኮነ በኀቤክሙ ወአፍ
ቅሮትክሙ ኪያነ ከማሁ አፈድፍዱ ካዕበ ውስተ
ዛቲ ጸጋ ።
፰ ወአኮ በግብር ዘእብለክሙ ዳእሙ እስመ በ እለ ይጽ
ሕቅዎ ለዝንቱ እምኔክሙ ወናሁ አአመርኩ ጽንዐ
ሃይማኖትክሙ ።
፱ ተአምሩ ጸጋሁ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ በእን
ቲአክሙ እንደየ ርእሶ እንዘ ባዕል ውእቱ ከመ አን
ትሙ ትብዐሉ በንዴተ ዚአሁ ።

፲ ወበዝንቱ አምክርኩክሙ ዘይበቍዐክሙ ወአቅደም
ክሙ ትመጥዉ ነፍሰክሙ እምቀዳሚ ዓም ።

፲፩ ወይእዜሰ ግበሩሂ ወፈጽሙሂ እስመ ፈቂድሂ እምፈ
ቲው ወገቢርሂ እምረኪብ ።
፲፪ ወእምከመሰ ፈቂድ ሀሎ ይትመዘገን በዘይትከሀሎ ፤
ወአኮ በአምጣነ ዘኢይትክሃሎ ።
፲፫ ወአኮ ከመ በዕድ ያዕርፍ ኪያክሙ ዘናጠውቅ ዳእሙ
ተሀልዉ ዕሩየ በዝ መዋዕል ።

ቁንም ቲቶን ደስ ስለ አለው ደስ አለን በሁላችሁ ዘን
ድ ሰውነቱን አሳርፋችኋታልና ። ሮሜ ፲፭ ፴፪ ።
ስለ እናንተ በተመካሁበት ሁሉ አላሳፈራችሁኝ ፲፬
ምና የነገርነውን እውነት አደረጋችሁልን ፤ እንዳል
ነውም እውነት ሆነ ።
እንደምትታዘዙለት እየፈራችሁ እየደነገጣችሁ እንደ ፲፭
ምትቀበሉት እያሰበ እጅግ ያመሰግናችኋል ። ፊል
፪ ፲፪ ፡ ምዕ ፪ ፱ ።
በሁሉም እተማመናችኋለሁና ደስ ይለኛል ። ፲፮

ምዕራፍ ፰ ።

<u>ክፍል ፱ ፡ ማዋጣት እንዲገባ ።</u>

ወንድሞቻችን ! በመቄዶንያ ላሉችው ቤተ ክርስቲያን ፩
የተሰጠውን የእግዚአብሔርን ጸጋ እነግራችኋ
ለሁ ። ሮሜ ፲፭ ፳፮ ። ፩ ቆሮ ፲፮ ፩ ።
በመከራ ብዙ ከመፈተናቸው የተነሣ ደስታቸው ፪
በዝቷልና ፡ እንደ ችግራቸው ዕናት እንስጥ ማለታ
ቸው በዝታለችና ። ማር ፲፪ ፵፬ ።
እነሱ ቢቻላቸው በይቻላቸውም ቈራጦች ለመሆና ፫
ቸው ምስክራቸው እኔ ነኝና ።
የቅዱሳንን አገልግሎት ስለ መሳተፍ መላልሰው ማለ ፬
ዱን ። ምዕ ፱ ፩ ። ግብ ሐዋ ፲፩ ፳፱ ።
እኛ እንዳሰብነው እንኳ አይደለም እነሱ አስቀድመው ፭
በፈቃዳቸው ሰውነታቸውን ለእግዚአብሔር አሳል
ፈው ሰጥተዋልና ። ፩ ሳሙ ፩ ፳፰ ።
ቲቶ ደስ አሰኝቶናልና እንደ ጀመረ ደግነቱን ይፈ ፮
ጽምላችሁ ዘንድ ማለድነው ። ምዕ ፲፪ ፲፰ ።
በፍጹም ሃይማኖት በአነጋገር በእውነት በትጋት ፯
በእናንተ ዘንድ በሆነው ሁሉ ፍጹማን ሆናችኋልና
እኛን እንደወደዳችሁ እንዲሁ ይህችን ስጦታ
አብዙ ። መዝ ፻፲፪ ፱ ። ምሳ ፳፪ ፱ ። ፩ ቆሮ ፩ ፭ ።
በግድ የምላችሁ አይደለም ከእናንተ ለዚህ ሥራ ፰
የሚተጉለት ስላሉ ነው እንጂ ፡ የሃይማኖታችሁን የፍ
ቅራችሁን ዕናት አሁን አወቅሁ ። ፩ ቆሮ ፯ ፮ ።
የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስን ቸርነት ታውቃላችሁ ፱
የባሕርይ ባለጸጋ ሲሆን ስለ እናንተ ራሱን ድኻ እን
ዳሰኘ በእሱ ድኽነት እናንተ ትከብሩ ዘንድ ። ማቴ
፰ ፳ ። ፊል ፪ ፮ - ፯ ።
በዚህም የሚጠቅማችሁን ነገርኋችሁ ከድሮ ዘመን ፲
ጀምሮ ሰውነታችሁን አሳልፋችሁ ልትሰጡ ወዳችኋልና ። ምሳ ፲፱ ፲፯ ። ፩ ቆሮ ፯ ፳፭ ።
አሁንም ሥሩ ፈጽሙ ልስጥ ማለት ከመሻት ነውና ፲፩
መስጠትም ከማግኘት ነውና ።
ልስጥ ማለት ካለ በሚቻለው ይመሰገናል በማይቻ ፲፪
ለው መጠን አይደለም ። ምሳ ፫ ፳፰ ። ማር ፲፪ ፵፫
ሌላው እንዲያርፍ እናንተን የምናስጨንቅ አይደለም ፲፫
በዘመኑ ሁሉ በመተካከል እንድትኖሩ ነው እንጂ ።

፲፬ እስመ ተረፈ ዚአክሙ ውስተ ንትጋ እልክቱ ይከ
ውን፡ ወተረፈ ዚአሆሙ ውስተ ዚአክሙ ከመ ይኩን
ሀልዎትክሙ ዕሩየ በኵሉ ።
፲፭ እስመ ከመዝ ይቤ መጽሐፍ ዘበ ብዙኅ ኢያትረፈ
ወዘበ ውኁድ ኢያሕፀፀ ።

ክፍል ፲ወ፩ ፡ በእንተ አርእዮ ፍቅር ለምእመናን ።

፲፮ እኩት እግዚአብሔር ዘወሀበነ ለነሂ ንጽሐቀ በእንቲ
አክሙ በከመ ይቤ ቲቶ ።
፲፯ እስመ የአኀተክሙ ወተወክፈ ለክሙ ሥላጤክሙ
ወአስተፋጠነ ይምጻእ ኀቤክሙ ጥቡዐ ።
፲፰ ወፈነውነ ምስሌሁ እኅነ ዘንእድዎ ኵሉ አብያተ
ክርስቲያናት በእንተ ትምህርቱ ።
፲፱ ዓዲ ሥዩም ውእቱ ለቤተ ክርስቲያን ወኅቡር ምስ
ሌነ በዛቲ ጸጋ እንተ ተልእክነ ለስብሐተ እግዚአብ
ሔር ከመ ንትፈሣሕ ።
፳ ወተዐቀብዎ ለዝንቱ ከመ ኢትንውርዋ ለመልእክ
ትክሙ ።
፳፩ ወሠናየ ሐልዩ ለቅድመ እግዚአብሔር ወለቅድመ
ሰብእ ።
፳፪ ወናሁ ፈነውነ ምስሌሆሙ ዓዲ እኅነ ዘአመከርናሁ
በብዙኅ ወረከብናሁ ከመ ጽሑቂ ውእቱ በኵሉ ፡ ወይ
እዜኒ ፈድፋደ ያስተፋጥን ይምጻእ ኀቤክሙ ወይጽ
ሕቀ በእንቲአክሙ እስመ ብዙኃ ያፈቅረክሙ ።
፳፫ ወእመኒ ቲቶ ሱታፌ ዘነኀብር ግብረ ምስሌሁ ወአኀ
ዊነ ሐዋርያት ዘቤተ ክርስቲያን ለስብሐተ እግዚአ
ሔር ።
፳፬ ወይእዜሰ አርእዩ ሎሙ ክሡተ ተፋቅሮተክሙ
ዝንቱ ውእቱ ዘበቱ ንትሜካሕ ብክሙ ንሕነ፡ ወይእ
ዜኒ አርእዩ በሙ በቅድመ ቤተ ክርስቲያን ።

ምዕራፍ ፱ ።

ክፍል ፲ወ፪ ፡ ዘከመ ይደሉ አስተዋጽኦ በፈቂድ ።

፩ ወበእንተሰ መልእክተ ቅዱሳን ብዙኅ ብየ ዘእጽሕፍ
ለክሙ ።
፪ እስመ አእመርኩ ከመ ትጽሕቁ አንትሙ ወበእን
ተዝ ንእድኩክሙ በኀበ ሰብአ መቄዶንያ ወእቤ
ሎሙ እስመ ሰብአ አካይያ አስተዳለዉ እምቀዳሚ
ዓም ወናሁ አጽሐቆሙ ተቃሕዎተ ዚአክሙ ለብዙ
ኃን ሰብእ ።
፫ ወፈነውናሆሙ ለአኅው ከመ ኢይኩነነ ሐሰተ በኀ
ቤሆሙ ዘንእድናክሙ በዝንቱ ወከመ ይርከቡክሙ
ድልዋኒክሙ በከመ ንቤሎሙ ።
፬ ወእመበ ከመ መጽኡ ምስሌየ ሰብአ መቄዶንያ ወረ
ከቡክሙ ዘእንበለ ታስተዳልዉ ንትኀፈር ንሕነኒ ወለ
ክሙኒ ከመ ኢይበሉክሙ አስተትክሙ ።
፭ አስተበቍዐክሙ አኀዊነ ግብረ ረስይዎ ወአስተዳ



የእናንተ ፍጹምነት የነዚያን ጉድለት ይመላልና፡ የነ ፲፬
ሱም ፍጹምነት የእናንተን ጉድለት ይመላልና፡ ኑሮ
አችሁ በሁሉ ትክክል ይሆን ዘንድ ። ምዕ ፱ ፲፪ ።
መጽሐፍ "ብዙ ያለው አላተረፈም ጥቂት ያለው አላ ፲፭
ጐደለም" ብሏልና ። ዘፀ ፲፮ ፲፰ ።

ክፍል ፲፩ ፡ ለምእመናን ፍቅርን ስለ መግለጽ ።

ቲቶ እንደ ተናገረ ስለናንተ እንድናስብ ያደረገን እግ ፲፮
ዚአብሔር ይክበር ይመስገን ። ምዕ ፱ ፲፭ ።
ያመሰግናችኋልና ፍጹምነታችሁንም ወዶላችኋልና ፲፯
ጨክኖ ወደ እናንተ ሊመጣ ቸኵሏል ።
ስለ ትምህርቱ ምእመናን ሁሉ ያመሰገኑትን ወንድ ፲፰
ማችንንም ከእሱ ጋር ልከናል ። ምዕ ፲፪ ፲፰ ።
ወዲህም የቤተ ክርስቲያን ሹም ነው ፡ ደስ ይለን ፲፱
ዘንድ እግዚአብሔርን ለማመስገን በምናገለግልበት
በዚች ጸጋም ከእኛ ጋር አንድ ነው ። ምዕ ፬ ፲፭ ።
መልእክታችሁንም እንዳታስነቅፉ ይህን ጠብቁ ። ፳
ኤፌ ፭ ፲፭ ።
ለሰውም ለእግዚአብሔርም መልካሙን ነገር አስቡ ። ፳፩
ምሳ ፫ ፬ ። ማቴ ፭ ፲፯ ።
ከነሱም ጋር በብዙ የፈተነውን በሁሉ ትጉህ ሁኖ ፳፪
ያገኘነውን ወንድማችንን ደግሞ አሁን ልከናል አሁ
ንም ወደ እናንተ ሊመጣ እጅግ ይፋጠናል ስለ እና
ንተም እጅግ ያስባል ይወዳችኋልና ።
በሥራ የምንተባበረው ቲቶም ቢሆን ወንድሞቻችን ፳፫
ሐዋርያትም ቢሆኑ ለእግዚአብሔር ክብር የቤተ ክር
ስቲያን ሹማምንት ናቸው ። ሮሜ ፲፮ ፯ ።
አሁንም ፍቅራችሁን በግልጥ አሳዩአቸው እኛ በእ ፳፬
ናንተ የምንመካበት ሥራ ይህ ነው ። አሁንም በም
እመናን ፊት ግለጡላቸው ። ምዕ ፯ ፲፬ ።

ምዕራፍ ፱ ።

ክፍል ፲፪ ፡ በፈቃድ ማዋጣት እንደሚገባ ።

ለቅዱሳን ስለሚደረገው አገልግሎት የምጽፍላችሁ ፩
ብዙ አለኝ ። ምዕ ፰ ፬ - ፭ ።
እናንተም እንደምትተጉ አውቃለሁና ስለዚህም ፪
የአካይያ ሰዎች ከዓምና ጀምሮ ገንዘብ አዘጋጅ
ተዋል ብዬ በመቄዶንያ ሰዎች ዘንድ አመሰግን
ኋችሁ ብዙዎችን ሰዎችን ከእናንተ ጋር መፈክ
ከር አትግቷቸዋልና ።
በዚህም ያመሰገንናችሁ ምስጋና በእነሱ ዘንድ ሐሰት ፫
እንዳይሆን እንደ ነገርናቸው ተዘጋጅታሁ ያገኟችሁ
ዘንድ ወንድሞቻችንን ላክን ። ምዕ ፰ ፳፬ ።
ምናልባት የመቄዶንያ ሰዎች ከእኔ ጋር የመጡ እን ፬
ደሆነ ገንዘቡን ሳታዘጋጁ ቢያገኙዋችሁ እኛም እናፍ
ራለን እናንተም ሥራት አፈረሳችሁ እንዳይሏችሁ ።
ወንድሞቻችን ፡ ይህን ግድ አድርጉት ብዬ አማልዳች ፭

ልዑ. ውእተ በረከተክሙ ወሥርዑ ዘነገርኩክሙ እንተ ላቲ ድልዋን አንትሙ፡ ወከመዝ ረስዩዎ ከመ ዘበረከት ወአኮ ከመ ዘበ ትዕግልት ።

፮ ወዘሰ ጠዊዖ ይዘርእ ለዝንቱ ከማሁ ይጠውዖ ሎቱኒ ማእረሩ ፡ ወዘሰ በበረከት ይዘርእ በበረከት የአርር ።

፯ ወኵሉ በከመ አደሞ ልቡ ለይግበር እስመ ኢኮነ በአገብሮ ዳእሙ በፍሥሐ ለየሀቡ ፡ እስመ ከማሁ ያፈ. ቅር እግዚአብሔር ።

፰ ወይክል እግዚአብሔር አፈድፍዶ ለክሙ ኵሎ በረከቶ ያብዝኅ ለዝሉፉ ወታተርፍዎ ለኵሉ ወታፈደፍዱ በኵሉ በምግባረ ሠናይ ።

፱ በከመ ይቤ መጽሐፍ ዘረወ ወወሀበ ለነዳይ ፡ ወጽድቁኒ ይነብር ለዓለም ።

፲ ወውእቱ ይሁብ ዘርአ ለዘራኢ ወእክለ ለሲሳይ ያሠምር ወያበዝኅ ለክሙ ማእረረ ጽድቅክሙ ።

፲፩ ከመ ትብዐሉ በኵሉ ትፍሥሕት እንተ ትገብር ለክሙ አኰቴተ እግዚአብሔር በእንተ ብዙኃን ።

፲፪ እስመ ዛቲ መልእክተ ዝንቱ ግብር አኮ ለዝንቱ በሕቲቱ ዘታሠልጥ እስመ ትፈጽም ሎሙ ተፅናሰሙ ለቅዱሳን ዓዲ ወታፈደፍድ አኰቴተ እግዚአብሔር በላዕለ ቅዱሳን ።

፲፫ ወየአኵትዎ ለእግዚአብሔር በመከራሂ ለዛቲ ሃይማኖትክሙ እስመ ተአመንክሙ ለመልእክተ ክርስቶስ ወኅበርክሙ ተፈሢሐክሙ ወአስተዋፃእክሙ ኵልክሙ ።

፲፬ ወእሙንቱኒ ይጼልዩ በእንቲአክሙ ወይፈትዉ ይርአዩክሙ በእንተ ጸጋ እግዚአብሔር ዘላዕሌክሙ ።

፲፭ አኰቴት እግዚአብሔር በእንተ ጸጋሁ ኢትትረከም ወትመጽእ እመ ኢትሐዘብዋ ።

ምዕራፍ ፲ ።

<u>ክፍል ፲ወ፫ ፡ በእንተ ኃይለ እግዚአብሔር ።</u>

፩ አስተበቍዐክሙ አኅዊነ አነ ጳውሎስ በየውሃት ወበ ምሕረተ ክርስቶስ እስመ ሰበ እሄሉ ኀቤክሙ መጠነ በገጽ ወበኀበሰ ኢሀሎኩ እተፈ ላዕሌክሙ ብቍዑኒ እሕመ እንዘ ኢሀሎኩ ትትአመን በአፍቅሮትክሙ ።

፪ ከመ ኢይሥራሕ እመ መጻእኩ ኀቤክሙ ወእትኀበል አጥብዕ እስመ ብ እለ ይትሔዘቡነ ከመ በሕገ ሥጋ ነሐውር ።

፫ በሥጋነሰ ነሐውር ወአኮ በሕገ ዚአሁ ዘነሐውር ወዘ ንፀብእ ።

ኋለሁ ይህንንም በረከት የምታገኙበትን አዘጋጁ እና ንተ የተዘጋጃችሁላትን የነገርኳችሁን ፈጽሙ እንዲህ አድርጉት ተቀምቶ እንደሄደባችሁ ሳይሆን በረከት የምታገኙበት እንደመሆኑ አድርጉ ብዬ እነግራችኋለሁ ።

አሳንሶ የሚዘራ እንዲሁ መከሩ ያንስበታል ፡ አብዝቶ የዘራ ግን በብዙ ያመርታል ። ምሳ ፲፩ ፳፬ ። ፲፱ ፲፯ ። መክ ፲፩ ፩-፯ ። ሉቃ ፯ ፴፰ ። ። ፮

ሁሉ ልቡ እንደወደደ ያድርግ ደስ ብሏቸው ይስጡ እንጂ በግድ አይደለምና እግዚአብሔር እንዲህ ያለ ውን ስጦታ ይወዳልና ። ዘፀ ፳፭ ፪ ። ዘዳግ ፲፭ ፯ ። ፯

እግዚአብሔር ሁል ጊዜ ፍጹም በረከቱን ሊያበዛላችሁ ይችላል እናንተም በፍጹም ምግባር አብዝታችሁ ለሁሉ ታተርፉታላችሁ ። መዝ ፹፱ ፲፩ ። ፰

መጽሐፍ "በተነ ለድኃ ሰጠ ፡ ጽድቁም ለዘለዓለም ይኖራል" ብሎ እንደ ተናገረ ። መዝ ፻፲፪ ፱ ። ፱

እርሱ ዘርን ለዘሪ እህልንም ለተመጋቢ ይሰጣል የጽድቃችሁንም አዝመራ ያሠምርላችኋል ያበዛላችኋል ። ዘፍ ፩ ፲፩-፲፪ ። ኢሳ ፶፭ ፲ ። ሆሴዕ ፲ ፲፪ ። ፲

ስብዙ ሰዎች ስለ ሰጣችሁ የእግዚአብሔርን ምስጋና በምታደርግላችሁ በፍጹም ደስታ ትከብሩ ዘንድ ። ፲፩

ስለዚህ ሥራ የምትደረገው ይህቺን አገልግሎት ግዳጅ የምትፈጽም ለዚህ ብቻ አይደለም የቅዱሳንን ችግር ታሟላለችና በቅዱሳንም ዘንድ የእግዚአብሔርን ምስጋና ታበዛለችና ። ምሳ ፰ ፲፬ ። ፲፪

በዚች በሃይማኖታችሁ ፈተና ምክንያት እግዚአብሔርን ያመሰግኑታል ክርስቶስ ላስተማራት ትምህርት ታዝዛችኋልና ሁላችሁም ደስ ብሏችሁ ተባብራችሁ አወጣጥታችኋልና ። ፲፫

እነሱም ስለ እናንተ ይጸልያሉ ስለ አደረችባችሁ የእግዚአብሔር ጸጋም ሊያዩአችሁ ይመኛሉ ። ማቴ ፭ ፲፯ ። ዕብ ፲፫ ፲፯ ። ፲፬

ስለማትመረመር ባላሰቢትም ጊዜ ስለምትመጣ ጸጋው ፡ እግዚአብሔር የተመሰገነ ነው ። ያዕ ፩ ፲፯ ። ፲፭

ምዕራፍ ፲ ።

<u>ክፍል ፲፫ ፡ ስለ እግዚአብሔር ኃይል ።</u>

ወንድሞቻችን ! እኔ ጳውሎስ በክርስቶስ ቸርነትና በደግነቱ እማልዳችኋለሁ ከእናንተ ዘንድ በነበርኩ ጊዜ ከፊታችሁ የመኖሬን ያህል በቃል እነግራችኋለሁ ፡ በሌለሁበት ጊዜ ግን እጽፍላችኋለሁ በጂ በሉኝ ፡ ሳልኖርም እንደምትወዱኝ አምናለሁና ። ፪ ቆሮ ፪-፫ ። ፩

ወደ እናንተ በመጣሁ ጊዜ እንዳልደክም በሥጋዊ ሥራት እንደምንኖር አድርገው የሚጠረጥሩን አሉና ጨክኜ እሠራለሁ ። ቍ ፲፩ ። ፪

በሥጋችንስ እንኖራለን ፡ ግን በእሱ ሕግ የምንኖር የምንዋጋ አይደለም ። ፫

፩ እስመ ንዋየ ሐቅሉ ለፀብእነ ኢኮነ በሕገ ሥጋ አላ
በኃይለ እግዚአብሔር ውእቱ ዘይነሥት አጽዋናተ
ፀሩዓን ።
፭ ወያንህል ኵሎ ዘይትዔበይ ወይትሌዓል ላዕለ ክርስ
ቶስ ከመ ይፄወው ኵሎ ልብ ወሕሊና ይግነይ ለእ
ግዚአብሔር ።
፮ ወድልዋን ንሕነ ንትበቀሎ ለዘኢይገርር ወኢይሰምዕ
ሶበ ፈጸምክሙ አንትሙ ትእዛዘ ዘመንገለ ገጽ
ርእዩ ዘቅድሜክሙ ።
፯ ወዘሂ ተአመነ በክርስቶስ ከመዝ ለየሐሊ ለሊሁ
እስመ በከመ ክርስቶስ ከማሁ ንሕነሂ ።
፰ ወእመኒ ዘተመከሕኩ ፈቂድየ በሚመትክሙ እንተ
ወሀበኒ እግዚአብሔር ለተሐንፆትክሙ ወአኮ ለተነ
ሥቶ ኢይትኀፈር ።
፱ ወበሕቱ እምህክ ዘንተ ከመ ኢይምሰሎ ለዘይትሐ
ዘብ ከመ ዘአኔርመክሙ በመጻሕፍትየ ።
፲ እስመበ እምሰብእ ዘይብል እስመ መጻሕፍቲሁሰ
ክቡዳት ወዕፁባት ወሀልዎቱሰ በሥጋ ድኩም ውእቱ
ወነገሩሂ ሕፁር ።
፲፩ ወበሕቱ ዘንተ ነገረ ያእምር ዘይቄል ዘንተ ከመ በቃ
ልነ በውስተ መጻሕፍት እመ ኢሀለውነ ከማሁ በም
ግባርነሂ እመ ሀለውነ ።
፲፪ ወኢንትሃበል ናጥብዕ ነሐሊ ሰርእስነ ለሊነ ከመ
እለ ይንእዱ ርእሶሙ በዘእሙከሩ ወአየኑ ለሊሆሙ
ወኢየአምሩ ፍካሬሁ ዘለሊሆሙ ይነብቡ ።
፲፫ ወንሕነሰ ኢንትመከሕ ፈድፋደ እምዐቅምነ ዘእንበለ
በመስፈርት ወሕግ ዘአቀመ ለነ እግዚአብሔር እስከ
ንበጽሕ ኀቤክሙ ።
፲፬ እስመ አኮ ዘንዌድስ ርእሰነ ከመ ዘኢበጻሕነ ኀቤ
ክሙ ዳእሙ በጻሕነ ኀቤክሙ ውስተ ትምህርተ ክር
ስቶስ ።
፲፭ ወንሕነሰ ኢንትሜክሕ በዘኢይረትዕ በፃማ ነኪር
ወበሕቱ ንሴፎ ትብዛኀ ሃይማኖትክሙ ወትዕበይ በላ
ዕሌክሙ ሕገ ሥርዓትክሙ ።
፲፮ ወፈድፋደ ንሜህረክሙ ወእሜሃ የዐቢ ምስሌሁ
አምጣንነ ወንሕነሰ ኢንትሜከሕ በዘኢይረትዕ ወበ
ዘኢይደሉ ።
፲፯ ወዘሰ ይትሜካሕ በእግዚአብሔር ለይትመካሕ ።
፲፰ ወአኮ ዳእሙ ዘርእሶ ንእደ ኅሩየ ይከውን ፡ አኮኑ
ዘእግዚአብሔር ንእዶ ከመ ።

የሰልፋችን መሣሪያ ዕኑ ዕኑ አምባዎችን በሚያፈርስ ፩
በእግዚአብሔር ኃይል ነው እንጂ በሥጋ ሥርዓት
አይደለምና ። ኤር ፩ ፲ ። ኤፌ ፮ ፲፫ - ፲፯ ።
በክርስቶስ ላይ የሚታበየውንና ከፍ ከፍ የሚለውን ፭
ሁሉ በሚያጠፋ ልብ ሁሉ ያምን ዘንድ ሐሊናም
ሁሉ ለእግዚአብሔር ይገዛ ዘንድ ።
ሰምቶ የማይታዘዘውን ልንበቀለው ዝግጁዎች ነን ፮
ወደፊት እንድትሄዱ የሚያደርጋችሁን ትእዛዝ በፈ
ጸማችሁ ጊዜ ወደ ፊታችሁ ተመልከቱ ። ኤር ፳ ፩ ።
በክርስቶስ ያመነ ሰው እርሱ እንዲህ ያስብ ፡ እኛም ፯
እንደዚሁ እንደ ክርስቶስ ነንና ። ምዕ ፲፩ ፳፫ ።
ለማፍረስ ያይደለ እናንተን ለማነፅ እግዚአብሔር ለሰ ፰
ጠኝ ሹመት የተመከሁት ትምክሕት ቢኖር አላፍ
ርም ። ምዕ ፲፪ ፯ ። ፩ ቆሮ ፭ ፪ ። ፬ ፭ ።
ግን ለሚጠራጠር ሰው በመጻሕፍቶቼ የማስፈራራ ፱
እንዳይመስለው ይህን እተወዋለሁ ።
ከሰዎች መካከል መጻሕፍቶቹ ከበዶች አስጨናቂ ፲
ዎች ናቸው በሥጋ አኗኗሩ ግን ደካማ ነው ፡ ነገሩም
ተርታ ነው የሚል አለና ። ገላ ፬ ፲፫ ። ቀ ፩ ።
ነገር ግን ይህን የሚል በሌለንበት ጊዜ በመጻሕፍት ፲፩
እንደሚገለጠው እንደ አነጋገራችን ባለን ጊዜም
በሥራችን እንዲሁ እንደሆነ ይህን ነገር ይወቅ ።
ራሳቸው በአሰቡት በገመገሙት መጠን ራሳቸውን ፲፪
እንደሚያመሰግኑ ራሳቸውም የሚናገሩትን ትርጓሜ
ውን እንደማያውቁ ሰዎች አድርገን ለራሳችን ልና
ስብ ፈጽሞ አንሞክርም ። ምዕ ፫ ፩ ። ፭ ፲፪ ።
እኛስ ወደ እናንተ እስክንደርስ ድረስ እግዚአብ ፲፫
ሔር በወሰነልን ሕግና ሥርዓት እንጂ ከዓቅማችን
አልፈን አንመካም ። ሮሜ ፲፪ ፫ ።
ወደ እናንተ እንዳልደረስን አድርገን ራሳችንን የምና ፲፬
መሰግን አይደለምና ፡ የክርስቶስን ሕግ በማስተማር
ወደ እናንተ ደርሰናል እንጂ ። ፩ ቆሮ ፱ ፩ ።
እኛስ በማይገባው ሌላ በደከመበት አንመካም ፡ ነገር ፲፭
ግን ሃይማኖታችሁ እንድትሰፋ የተሠራችላችሁ
ሕግም በእናንተ ላይ እንድትፀና ተስፋ እናደርጋ
ለን ። ሮሜ ፲፭ ፳ ።
አብዝተንም እናስተምራችኋለን ያን ጊዜ መጠናችን ፲፮
ከሥራችን ጋር ከፍ ከፍ ይላል እኛስ በማይቀናና
በማይገባ አንመካም ።
የሚመካ ግን በእግዚአብሔር ይመካ ። ኤር ፱ ፳፫ - ፲፯
፳፬ ። ፩ ቆሮ ፩ ፴፩ ።
ራሱን ያከበረ ብቻ የሚከብር አይደለም ፡ እግዚአብ ፲፰
ሔር ያከበረው ይከብራል እንጂ ። ሉቃ ፲፰ ፲፬ ።

## ምዕራፍ ፲ወ፩ ።

### ክፍል ፲ወ፬ ፡ በእንተ ኢ.ተወክፎ ትምህርተ በዕድ።

፩ ወርቱዕሰ ትትዐገሡኒ ኅዳጠ ከመ እንብብ በዕበድየ
እንዘ ትትዔገሡኒ ።
፪ እስመ እቀንእ ለክሙ ቅንአተ እግዚአብሔር እስመ
ፈነርኩክሙ ለአሐዱ ምት ድንግል ወንጹሐ ክርስ
ቶስ ከመ አቅርብክሙ ኀቤሁ ።
፫ ወባሕቱ እፈርሀ ዮጊ ከመ አርዌ ምድር አስሐታ
ለሔዋን በጕኅሉት እንዳዒ ለእመ ይማስን ልብክሙ
እምየውሀቱ ወንጽሐ ለክርስቶስ ።

፬ ሶበሁ ከነ ዘይመጽእ ኀቤክሙ ዘጸውዐክሙ ኀበ
ካልእ ዘኢሰበክነ ለክሙ ፡ ወእመበ ካልእ መንፈስ
ዘትነሥኡ ዘኢነሣእክሙ ፡ ወእመኒበ ካልእ ትምህርት
ዘኢተመሀርክሙ ርቱዕ ትጽንሑነ ።
፭ ወባሕቱ እትሔዘብ አልቦ ዘአሕፀፅኩክሙ ዘእምበ
ዕዳን ሐዋርያት ።
፮ ወእመኒ ዐብድ አነ በቃልየ አኮኬ በልብየ ወባሕቱ
አከሥት ለክሙ ኵሎ ውስተ ኵሉ ።
፯ ወሚመ አበስኩኑ እንጋ ዘአሕመምኩ ርእስየ በኵሉ
ከመ አንትሙ ትትለዐሉ እስመ በከንቱ መሀርኩ
ክሙ ትምህርተ እግዚአብሔር ።
፰ ወባዕደሰ ቤተ ክርስቲያን ቀሠጥኩ ወነሣእኩ ለሲሳ
ይየ ከመ እትለአክሙ ወአመሂ ሀለውኩ ኀቤክሙ
ኢተሰቆቁ ንዋየክሙ እንዘ እጼነስ ።
፱ ወኀበሂ ኢያእከልኩ ሠለጡ ሊተ አኀዊነ በጺሐሙ
እመቄዶንያ ወበኵሉ ተዐቀብኩ ከመ ኢያክብድ ላዕ
ሌክሙ ወእትዐቀብ ።
፲ እስመ ጽድቁ ለክርስቶስ ይሄሉ ምስሌየ ወኢተዐፅ
ወተኒ ዛቲ ፍሥሐየ በደወለ አካይያ ።
፲፩ በእንተ ምንት እስመሁ እንጋ ኢያፈቅረክሙኑ እን
ከሰ እግዚአብሔር የአምር ዘንተ ።
፲፪ ወባሕቱ ዘሂ ገበርኩ ወዘሂ እገብር ከመ እክልአሙ
ምክንያተ ለእለ ይፈቅዱ ምክንያተ ከመ ኢይርከቡ
እሙንቱሂ በዘይትሜክሑ ከማነ ።
፲፫ እስመ ሀለዉ ሐሳውያን ገበርተ ዐመፃ እለ ይትሜ
የኑ ወይትሜሰሉ ሐዋርያተ ክርስቶስ ።
፲፬ ወዝኒ አኮ ለአንክሮ እስመ ለሊሁ ሰይጣን ይትሜሰል
ከመ መልአከ ብርሃን ።
፲፭ ወዝኒ ኢኮነ ዐቢየ ለእመ ይትሜሰሉ መላእክቲሁኒ
ከመ መላእክተ ጽድቅ ወደኃሪቶሙሰ በከመ ምግ
ባሮሙ ።

### ክፍል ፲ወ፭ ፡ በእንተ ዘኢርቱዕ ተመክሖ ።

፲፮ ወካዕበ እብል አልቦ ዘይሬስየኒ ከመ ዐብድ ወእመአ
ኮሰ ከመ ዐብድኒ ተወከፉኒ ከመ እትመካሕ አነሂ
ኅዳጠ ።

## ምዕራፍ ፲፩ ።

### ክፍል ፲፬ ፡ የባዕዳንን ትምህርት ስለ አለመቀበል ።

አገባብስ ጥቂት ልትታገሡኝ ይገባል ፡ ታግሣችሁኝ ፩
በስንፍናየ እናገር ዘንድ ። ምዕ ፭ ፲፫ ።
ለእግዚአብሔር የሚገባ ቅናት እቀናላችኋለሁ ወደ ፪
ርሱ አቀርባችሁ ዘንድ ለአንድ ንጹሕ ድንግል
ሙሽራ ለኢየሱስ ክርስቶስ አጭቻችኋለሁና ።
ነገር ግን ምናልባት የምድር እባብ ሔዋንን በተን ፫
ኰል እንዳሳታት እንደ ልቡናችሁ ከክርስቶስ ከደ
ግነቱ ከንጽሕናው ወጥቶ ይለወጥ እንደሆነ ብዬ እፈ
ራለሁ ። ዘፍ ፫ ፬ - ፲፫ ።
ወደናንት የሚመጣ እኛ ወደ አላስተማርናችሁ ወደ ፬
ሌላ ኢየሱስ የጠራችሁ ቢኖር ፡ ያልተቀበላችሁ የም
ትቀበሉት ሌላ መንፈስ ቢኖርም ያልተማራችሁት
ሌላ ትምህርት ቢኖርም እንኳ ልትጠብቁን ይገባል ።
ነገር ግን ከሌሎች ሐዋርያት ያጐደልኩባችሁ የሌለ ፭
ይመስለኛል ። ምዕ ፲፪ ፲፩ ። ፩ ቆሮ ፲፭ ፲ ።
እኔ በነጋገሬም አላዋቂ ብሆንም በልቤ አይደለም ፡ ፮
ግን ሁሉን በሁሉ እገልጥላችኋለ ሁ። ፩ ቆሮ ፪ ፩ ።
ወይስ እናንተ ከፍ ከፍ ትሉ ዘንድ በከንቱ የእግዚ ፯
አብሔርን ትምህርት ስለ አስተማርኋችሁ በሁሉ
ራሴን ያዋረድኩ በደልኩን ? ። ፩ ቆሮ ፱ ፲፪ - ፲፰ ።
ግን ከሌሎች ምእመናን እናንተን አገለግል ዘንድ ፰
ለምግቤ ያሀል ተቀበልኩ ፡ ከእናንተ ዘንድ በነበር
ኩበት ጊዜም ስቸገር ለገንዘባችሁ አልሳሳሁም ።
ባልበቃኝም ጊዜ ወንድሞቻችን ከመቄዶንያ መጥ ፱
ተው አሟሉልኝ እናንተን እንዳላስቸግራችሁ በሁሉ
ተጠነቀቅሁ ወደፊትም እጠነቀቃለሁ ። ምዕ ፲፪ ፲፫ ።
የክርስቶስ ጽድቁ አብሮኝ ይኖራልና ይህቺም ጸጋዬ ፲
በአካይያ አውራጃ አልተቋረጠችብኝም ።
ስለ ምን ነው ? አልወዳችሁምና ነውን ? እንጃ ፲፩
እንኪያስ እንደምወዳችሁ እግዚአብሔር ያውቃል ።
ግን ያደረግሁትም የማደርገውም ቢሆን ምክንያት ፲፪
ለሚሹት ሰዎች ምክንያትን አሳጣቸው ዘንድ ነው ፡
እነሱም እንደኛ የሚመኩበትን እንዳያገኙ ።
የሚተናኰሉ የክርስቶስ ሐዋርያት ነን የሚሉ በመ ፲፫
ፅን የሚያደርጉ ሐሰተኞች አሉና ። ምዕ ፪ ፲፯ ።
ይህም አያስደንቅም እሱ ራሱ ሰይጣን የብርሃን መል ፲፬
አክ መስሎ ይመጣልና ።
ይህም ታላቅ ነገር አይደለም የሰይጣን መልእክተ ፲፭
ኞች የእውነት መላእክትን ቢመስሉ ፍጻሜውያ
ቸው ግን እንደ ሥራቸው ነው ።

### ክፍል ፲፭ ፡ መመካት ስለማይገባ ።

ደግሞም እንዲህ እላለሁ ፡ እንደ ሰነፍ የሚቈጥረኝ ፲፮
አይኑር ያለዚያስ እንደ ሰነፍ እንኳ ብሆን ተቀበሉኝ
እኔም ጥቂት እመካ ዘንድ ። ምዕ ፲፪ ፮ ።

፲፯ ወዝኒ አኮ ዘመንገለ እግዚአብሔር ዘእነግር ዳእሙ
ከመ ዐብድ እዜንግዕ በእንተ ዛቲ ትምክሕትየ ።

፲፰ እስመ ብዙኃን እለ ይትሜክሑ በሕግ ዘሥጋ አነሂ
እትሜካሕ ።
፲፱ ወእመሰ ይኤድመክሙ አዕምኦቶሙ ለዐብዳን እንዘ
ጠቢባን ወነበብያን አንትሙ።
፳ እስመ ትትዔገሥዎሙ ለእለ ይትዔገሉክሙ ወለእ
ለሂ የኀይዱክሙ ለእለሂ ይበልዑክሙ ወለእለሂ
ይትዔበዩ ላዕሌክሙ ወለዘሂ ይጸፍዐክሙ ገጸክሙ ።
፳፩ እብል ዘንተ ከመ ዘያስተሐቅር ከመ ሕሙማኒሁ
ንሕነ ለክሙ እብል አነሂ በዕበድየ አልቦ ዘይትሐ
በል ላዕሌየ ዘእብል ዳእሙ ዘአነ እትሐበል ላዕሌሁ ።

፳፪ እመኒ ዕብራውያን እሙንቱ አነሂ ከማሆሙ ፡ ወእመኒ
እስራኤላውያን እሙንቱ አነሂ ከማሆሙ ፡ ወእመኒ
ዘርአ አብርሃም እሙንቱ አነሂ ከማሆሙ ።

፳፫ እመኒ ላእኩ ለክርስቶስ እሙንቱ አኮሁ እዜንግዕ
ለርእስየ በፃማሂ አፈድፈድኩ፡ ወበተቀሥፎሂ አፈድ
ፈድኩ ፡ ወበተሞቅሖሂ አብዛኅኩ ፡ ወለሞትኒ ብዙኃ
ተደለውኩ ።
፳፬ ኃምሰ ቀሠፉኒ አይሁድ በበአርባዓ ዘእንበለ አሐቲ ።
፳፭ ሥልሰ ዘበጡኒ በአብትር ፡ ምዕረ ወገሩኒ በእእባን ፡
ሥልሰ ሰኰየት ሐመርየ ፡ ቤትኩ ወወዐልኩ እንዘ
እጼብት ውስተ ዕመቀ ባሕር ።

፳፮ ወበመንገድሂ ዘልፈ እትመነደብ በተከዚነ አመንደ
ቡኒ ፈያት ፡ አመንደቡኒ አዝማድየ ፡ አመንደቡኒ አሕ
ዛብ ፡ ተመንደብኩ በሀገር ፡ ወተመንደብኩ በሐቅል
ተመንደብኩ በባሕር ፡ አመንደቡኒ ቢጽ ሐሳውያን ።

፳፯ በፃማ ወበሥራሕ ፡ ወበትጋሀ ብዙኅ ፡ በረኃብ ወበጽ
ምዕ ፡ በጾም ብዙኅ ወበቍር ወበዕርቃን ።

፳፰ ወዘእንበለዝ ብዙኅ ባዕድ ዘረከበኒ ኵሉ አሚረ እንዘ
እሔሊ ቤተ ክርስቲያናት ።
፳፱ መኑ ዘይደዊ ወኢየሐምም አነ ፡ ወመኑ ዘይስሕት
ወኢይደነግፅ ።
፴ ወእመሰ ይደሉ ተመክሖ ፡ አነኒ እትሜካሕ በሕማ
ምየ ።
፴፩ የአምር እግዚአብሔር አቡሁ ለእግዚእነ ኢየሱስ
ክርስቶስ ዘውእቱ አምላክ ቡሩክ ፡ ለዓለመ ዓለም
ከመ ኢይሔሱ ።
፴፪ በሀገረ ደማስቆ መልአከ አሕዛብ ዘእምታሕተ አርስ
ጣስዮስ ንጉሥ ዐቃቤ ሀገር ደማስቆናዊ ፈቀደ የአ
ኀዘኒ ።



ይህም የምናገረው በእግዚአብሔር ዘንድ የሚገባ ፲፯
አይደለም ፡ ስለዚህች መመከቴ እንደ ሰነፍ መምሰሌ
ነው እንጂ ። ምሳ ፱ ፬ ።
በሥጋዊ ሥርዓት የሚመኩ ብዙዎች ናቸውና እኔም ፲፰
እመካለሁ ። ኤር ፱ ፳፫ - ፳፬ ። ፊል ፫ ፫ ።
እናንተ ባለ አእምሮ ዐዋቂዎች ስትሆኑ ሰነፎቹን ፲፱
መስማት ደስ የሚያሰኛችሁ ከሆነ ።
የሚታገሷችሁን የሚቀሟችሁን የሚበድሏችሁን ፳
የሚታበዩባችሁን ፊታችሁን የሚመታችሁን ትታገ
ሷቸዋላችሁና ። ገላ ፪ ፬ ።
ይህን ንቆ እንደሚያቃልል ሰው እናገራለሁ እኛ ለና ፳፩
ንተ በሽተኞች መሆናችን ነውን ? እኔም ብሠለጥን
በት እንጂ የሚሠለጥንብኝ የለም እላለሁ ። ፩ ቆሮ
፩ ፲፯ ። ገላ ፬ ፲፫ ።
እነሱ ዕብራውያን ቢሆኑ እኔም እንደነሱ ዕብራዊ ፳፪
ነኝ ፡ እነሱ እስራኤላውያንም ቢሆኑ እኔም እንደነሱ
እስራኤላዊ ነኝ፡ እነሱ የአብርሃም ልጆች ቢሆኑ
እኔም እንደነሱ ነኝ ፊል ። ፫ ፭ ።
እነሱ የክርስቶስ አገልጋዮች ነን ቢሉ ለራሴ እዘነጋ ፳፫
የለምን ? በድካም ብዙ ደክሜያለሁ ፡ በመገረፍ ብዙ
ደክሜያለሁ ፡ በእሥራትም ብዙ ጊዜ ታሥሬአለሁ ፡
ለሞት ብዙ ጊዜ ተዘጋጅቼአለሁ ። ፩ ቆሮ ፲፭ ፪ ።
አንዲት ሳትቀር አምስት ጊዜ አርባ አርባ ገረፉኝ ። ፳፬
ሦስት ጊዜ በበትር ደበደቡኝ ፡ አንድ ጊዜ በድንጋይ ፳፭
ዮች ወገሩኝ ፡ መርከቤ ሦስት ጊዜ ተንከራተተች ፡
በጥልቁ ባሕር ሰዋኝ አድሬ ሰዋኝ ዋልኩ ። ግ. ሐ.
፲፬ ፲፱ ። ፲፮ ፳፪ ።
በጕዞም ዘወትር መከራ እቀበል ነበር በፈሳሽ ወኃም ፳፮
ወንበዶች አሠቃዩኝ ፡ ዘመዶቼም አስጨነቁኝ ፡ አሕዛ
ብም መከራ አፀኑብኝ ፡ በከተማ መከራ ተቀበልኩ ፡
በዱርም በባሕርም መከራ ተቀበልኩ ፡ ክርስቲያን
ነን ባዮችም መከራ አፀኑብኝ ።
በመውጣት በመውረድ ፡ በድካም በብዙ ትጋት ፳፯
በመራብ ፡ በመጠማት አብዝቶ በመጾም ፡ በመራቈት
በብርድ በዚህ ሁሉ መከራ ተቀበልኩ ። ምሳ ፮ ፩ ።
ከዚህም በቀር ለቤተ ክርስቲያን ሳስብ ዘወትር ያገ ፳፰
ኘኝ ልዩ ልዩ መከራ ብዙ ነው ። ግብ ሐዋ ፳ ፲፰ ።
ታሞ እኔ የማላዝንለት ማነው ? በድሎስ እኔ የማል ፳፱
ደነግጥለት ማነው ? ። ፩ ቆሮ ፱ ፳፪ ።
መመካት የሚገባስ ከሆነ እኔም በመከራዬ እመካለሁ ። ፴

ሐሰት እንዳልናገር ለዘለዓለም የባሕርይ አምላክ ፴፩
የሚሆን የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ አባቱ እግዚ
አብሔር ያውቃል ። ምሳ ፩ ፳፫ ።
በደማስቈ ከተማ ከአርስጣስዮስ ንጉሥ በታች ፴፪
የሚያዘው የሕዝብ ሹም አገር አሳዳሪ የነበረው የደ
ማስቆ ሰው ሊይዘኝ ወደደ ።

፴፫ ወአውረዱኒ በሰብሳብ እንተ መስኮት እምዓረፍት
ወአምሰጥኩ እምእዴሁ ።

ምዕራፍ ፲ወ፪ ።

ክፍል ፲ወ፩ ፤ በእንተ ዘከመ ኢይደሉ ተመክሐ ።

፩ ወናሁ ይረትዕ ሊተ ተመክሖ ወባሕቱ ኢኮነ ሠናየ፤
ንግባእ ካዕበ ወንዘክር ራእየ ዘከሠተ እግዚአብሔር ።

፪ አአምር ብእሴ ምእመነ በክርስቶስ እምቅድመ ዐሠ
ርቱ ወአርባዕቱ ዓመት እመኒ በሥጋሁ ወእመኒ ዘእ
ንበለ ሥጋሁ እንጃ እግዚአብሔር የአምር ወመሰ
ጥዎ ለውእቱ ብእሲ እስከ ሣልስ ሰማይ ።

፫ ወአአምሮ ለውእቱ ብእሲ እመኒ በሥጋሁ ወእመኒ
ዘእንበለ ሥጋሁ እንጃ እግዚአብሔር የአምር ።
፬ ወመሰጥዎ ውስተ ገነት ወሰምዐ ህየ ነገረ ዘኢይተ
ረጐም ዘኢይከውኖ ለእጓለ እመሕያው ይንብብ ።
፭ ወበእንተ ዝንቱኬ በዘከመዝ እትሜካሕ በርእስየ
ኢይትሜካሕ ዘእንበለ በሕማምየ ።
፮ ወእመኒ ፈቀድኩ እትመካሕ ኢኮንኩ ዓብደ እስመ
ጽድቀ እነግር፤ ወባሕቱ እምሕክ ከመ ኢይትሐዘቡኒ
በዘርእዩኒ ወበዘሰምዑኒ ፈድፋደ ።
፯ ወበእንተዝ ከመሰ ኢይትዐበይ በብዙኅ ራእይ ተው
ሀበኒ መልአከ ሰይጣን ዘይደጕፀኒ ሥጋየ ወይኰርዓኒ
ርእስየ ።
፰ ወአስተብቋዕክዎ ለእግዚእየ ሥልሰ በእንቲአሁ ከመ
ያእትቶ እምኔየ ።
፱ ወይቤለኒ የአክለከ ጸጋየ ወኃይልሰ በደዌ የሐልቅ
ወሠመርኩ እትመካሕ በሕማምየ ከመ ይኅድር
ኃይለ ክርስቶስ ላዕሌየ ።
፲ ወበእንተ ዝንቱ ሠመርኩ በሕማምየ በተጽዕሎሂ
ወበምንዳቤሂ ወበተሰዶሂ ወበተጽናስሂ በእንተ ክር
ስቶስ እስመ ሶበ አሐምም ሶቤሃ እፀንዕ ።

፲፩ ወናሁ ኮንኩ ዓብደ በተመክሖትየ በዘአንትሙ አገ
በርክሙኒ ወሊተሰ ርቱዕ እክበር በኀቤክሙ ወትኩ
ኑኒ ሰማዕትየ እስመ ዘአሕፀፅኩክሙ እምዘሖሩ
ሐዋርያት ወእመኒ ከመ ወኢምንት አነ ።

፲፪ ትምህርተ ሐዋርያትሰ ተገብረ ለክሙ በኵሉ ትዕግ
ሥት ወበተአምራት ወመንክራት ወኃይላት ።

፲፫ ወምንተኑ ዘአሕፀፅኩክሙ ወዘአኅጣእኩክሙ እም
ኵሉ ቤተ ክርስቲያናት ዘእንበለ ዛቲ እንተ ኢመጻ
እኩ ኀቤክሙ አሥርሕክሙ ጸግዉንያ ለዛቲ አበሳየ።
፲፬ ናሁ ሣልስየ ዝንቱ እንዘ አስተዳሉ እምጻእ ኀቤ
ክሙ ወኢተፋጠንኒ እስመ ኢያክሙ እፈቅድ ወአኮ

በቅርጫት አድርገው በመስኮቱ በኩል ከአጥሩ ላይ ፴፫
አወረዱኝና ከእጁ አመለጥኩ ግብ ሐ ፱ ፳፬-፳፭ ።

ምዕራፍ ፲፪ ።

ክፍል ፲፩፣ መመካት ስለ ማይገባ ።

እነሆ መመካት ይገባኛል ግን የሚገባ አይደለም ዳግ ፩
መኛም መለስ ብለን እግዚአብሔር የገለጠውን
ራእይ እናስታውስ ።
ከዐሥራ አራት ዓመት በፊት በክርስቶስ ያመነ አንድ ፪
ሰው ዐውቃለሁ በሥጋውም እንደሆነ ያለ ሥጋ
ውም እንደሆነ እንጃ እግዚአብሔር ያውቃል፣ያንን
ሰው እስከ ሦስተኛው ሰማይ ድረስ ነጥቀው ወሰ
ዱት ።
ያንን ሰው ዓውቀዋለሁ በሥጋው እንደሆነ ያለ ፫
ሥጋውም እንደሆነ እንጃ እግዚአብሔር ያውቃል ።
ወደ ገነትም ነጥቀው ወሰዱት በዚያም የማይተረ ፬
ጐም የሰው ልጅ ሊናገረው የማይቻለውን ነገር ሰማ።
ስለዚህ በእንደዚህ ያለው ነገር እመካለሁ በመከራዬ ፭
እንጂ በራሴ አልመካም ። ምዕ ፲፩ ፴ ።
ልመካም ብወድ አላዋቂ አይደለሁም እውነቱን እና ፮
ገራለሁና፣ ግን በዩኝ በሰሙኝ እጅግ እንዳይጠራጠ
ሩኝ ገምግሜ እተዋለሁ ። ምዕ ፲ ፰ ። ፲፩ ፲፮ ።
ስለዚህም ቢሆን በብዙ ራእይ እንዳልታበይ ሰውነ ፯
ቴን የሚወጋኝ ራሴን የሚቀጠቅጠኝ የሰይጣን መል
እክተኛ ተሰጠኝ ። ኢዮ ፪ ፯ ።
ከእኔ ያርቀው ዘንድ ስለ እርሱ ጌታዬን ሦስት ጊዜ ፰
ማለድኩት ። ዘዳግ ፫ ፳፫ ። ማቴ ፳፮ ፵፬ ።
ጸጋዬ ይበቃኻል ኃይልስ በደዌ ያልቃል የክርስ ፱
ቶስ ኃይሉ በእኔ ላይ ያድር ዘንድ በመከራዬ ደስ
ይለኛል ። መክ፡ ፯ ፲፰ ። ኢሳ፡ ፵ ፳፱ ።
ስለዚህም መከራዬ ልቀበል ወደድኩ በመሰደብም ፲
ቢሆን በመጨነቅም ቢሆን በመሰደብም ቢሆን ስለ
ክርስቶስ በመቸገርም ቢሆን መከራ በተቀበልኩ
ጊዜ ወዲያው እፀናለሁና ። ፊልጵ ፬ ፲፫ ።
እናንተ ስላገበራችሁኝ በመመካቴ እነሆ ሰነፍ ሆንኩ ፲፩
ለእኔማ እናንተ ምስክሮች ልትሆኑኝ በእናንተ ልክ
በር ይገባ ነበር እኔ እንደ ኢምንትም ብሆን ሐዋር
ያት ሁሉ ከሠሩት ሥራ ካስተማሩት ትምህርት ያጐ
ደልኩባችሁ የለምና ።
የሐዋርያት ትምህርትማ በፍጹም ትዕግሥት በተአ ፲፪
ምራት ድንቅ ሥራ በመሥራት ሙት በማስነሣት
ተደረገላችሁ ። ምዕ ፲፪ ፭ ።
ላስቸግራችሁ ካለመምጣቴ ከዚህች በቀር ከምእመ ፲፫
ናን ሁሉ ያሳጣኋችሁ ያጐደልኩባችሁ ምንድር
ነው ?, በደልህ ይህች ናት በሉኝ ። ምዕ ፲፩ ፱ ።
እነሆ ወደ እናንተ ልመጣ ስሰናዳ ይህ ሦስተኛዬ ነው፣ ፲፬
ግን አልተሳካልኝም ገንዘባችሁን ያይደለ እናንተን

ንዋየክሙ እስመ ርቱዕ አበው ይዝግቡ ለውሉ
ዶሙ ወአኮ ውሉድ ለአዝማዲሆሙ ።
፲፭ ወአንሰ ምክዕቢተ አስተዋፃእኩ ወእሚጡ ሥጋየ
በእንተ ነፍስክሙ ወእመኒ ፈድፋደ አፍቀርኩክሙ
ርእስየ አፍቀርኩ ።
፲፮ ወአንሰ ኢያክበድኩ ላዕሌክሙ ወባሕቱ መስተመይነ
ከዊንየ ነሣእኩክሙ በጕሕሉት ።
፲፯ በኑ እንጋ ዘፈነውኩ ኀቤክሙ ወበኑ ዘተበገልኩ
ክሙ ።
፲፰ ናሁ አስተብቋዕክዎ ለቲቶ ወፈነውክዎ ለካልእ እኁነ
ምስሌሁ በኑ ዘገፍዐክሙ ቲቶ አኮኑ በውእቱ መን
ፈስ ዘይረውፅ በላዕሌሁ በቱ ሖርነ ወአሠረ ዚአሁ
ተለውነ ።
፲፱ ትትሔዘቡነሁ ከመ ንሕነ ንትዋቀሥክሙ ዘኒ ንነግር ፥
በቅድመ እግዚአብሔር በእንተ ክርስቶስ ንነግር
ወዝንቱሰ ኵሉ አኃዊነ ከመ ትትሐነፁ ።

፳ ወባሕቱ እፈርህ ለእመበ ከመ አመ መጻእኩ ወኢ
ረከብኩክሙ በከመ እፈቅድ ወአነሂ እከውነክሙ
ከመ ዘኢትፈቅዱ ወዮጊ ይከውን ውስቴትክሙ
ተዝኅሮ ወተቃንኦ ወተምዕዖ ወተሣልቆ አው ተሐ
ምዮ ወተሀውኮ ወአዕብዮ ልብ ።

፳፩ ዮጊ ካዕበ መጺእየ ኃቤክሙ የሐምመኒ እግዚአብ
ሔር በእንቲአክሙ ወእላህዎሙ ለብዙኃን እለ
አበሱ ወኢነስሑ በእንተ ኀጣርሙ ወምርዓቶሙ
ወዝሙቶሙ ዘገብሩ ።

ምዕራፍ ፲ወ፫ ፤

፩ ወናሁ ሣልስየ ዝንቱ እንዘ እመጽእ ኀቤክሙ አኮኑ
በአፈ ክልኤቱ ወሠለስቱ ሰማዕት ይቀውም ኵሉ
ነገር ።
፪ ወአቀደምኩ ነጊረ እምትካት ወአቀድም ወእነግር
ዓዲ በከመ እቤለክሙ እንዘ ሀለውኩ በቀዳሚ
ከማሁ እንዘ ኢሀሎኩ በሣልስ እነግር ለእለ አበሱ
ቀዲሙ ወለባዕዳንሂ ከመ አመ መጻእኩ ኢይም
ሕክ እንከ ካዕበ ።
፫ እስመ ተኃሥሡ መከራሁ ለክርስቶስ ዘይነብብ በላ
ዕሌየ ውእቱ አልቦ ዘይሰአኖ በኀቤክሙ ዘእንበለ
ዳእሙ ኵሉ ዘይትከሀሎ ።
፬ እስመ ዘሐመ ወተሰቅለ በድካም ሕያው ውእቱ በኃ
ይለ እግዚአብሔር ፥ ወንሕነኒ ንደክም ምስሌሁ ወነ
ሐዩኒ ምስሌሁ በኃይለ እግዚአብሔር በእንቲአክሙ።

፭ ወርእሰክሙ አመክሩ ለእመ ሀለውክሙ በሃይማኖት
ወርእሰክሙ ሕቱ ለእመበ ዘኢተአምሩ ለሊክሙ
ወኢትጤይቁ ከመ ሀሎ ክርስቶስ ምስሌክሙ ወለእ
መሰ ኢኮነ ከመዝ ምኑናን አንትሙ ።

አሽለሁና ልጆች ለወላጆቻቸው ያይደለ አበቶች
ለልጆቻቸው ገንዘብ ሊያኖሩ ይገባልና ። ምሳ ፲፫ ፩።
እኔ ዕጽፍ ድርብ አወጣጣሁ ስለ ሕይወታችሁም ሕይ ፲፭
ወቴን አሳልፌ እሰጣለሁ እናንተን እጅግ ብወዳች
ሁም ራሴን መውደዴ ነው ። ፊልጵ ፱ ፲፮ ።
እኔ አላስቸገርኳችሁም ፥ ነገር ግን ብልህ ሆኜ በጥበብ ፲፮
ገንዘብ አደረግኋችሁ ።
በውኑ ወደ እናንተ የላክሁት መልእክት አለን? ፲፯
ወይስ የቀማኋችሁ አለን?።
እነሆ ቲቶን ማለድኩት ክርሱም ጋር ሌላውን ወን ፲፰
ድማችንን ላክሁት ፥ በውኑ ቲቶ የበደላችሁ በደል
አለን? ቲቶ በተቃኘበት መንፈስ የተቃኘን እሱ በሄደ
በት ፍለጋ የሄድን አይደለንም ። ምሳ ፰ ፯። ፲፮ ፲፰።
እኛስ እንደምንወቅሣችሁ ታስባላችሁን? በእግዚአ ፲፱
ብሔር ፊት የምንናገረውንም በክርስቶስ ፊት እንና
ገራለን፡ ወንድሞቻችን ይህ ሁሉ ግን እናንተ ትፀኑ
ዘንድ ነው ።
ነገር ግን ወደ እናንተ መጥቼ እንደምወደው ሆና ፳
ችሁ ያላገኘኋችሁ እንደሆነ፡ እኔም እንደማትወዱት
እሆንባችኋለሁ ፥ ወይም በመካከላችሁ ኵራት መቀና
ናት መበሳጨት መዘበበት ወይም መተማማት መታ
ወክ ልብን ማሳበጥ ይኖር ይሆናል ብዬ እፈራለሁ ።
ምሳ ፲ ፥ ፪። ፩ ቆሮ ፬ ፥ ፯ ።
ወይም እንደገና ወደ እናንተ መጥቼ እግዚአብሔር ፳፩
ያሳዝነኝ ይሆናል በድለው ስለ ጕስቍልናቸው ስለ
መዳራታቸው ስለሚሠሩት ዝሙታቸው ንስሐ ያል
ገቡትን እቀጣ ይሆናል ። ምሳ ፪ ፥ ፩ ። ፲፫ ፥ ፪ ።

ምዕራፍ ፲፫ ፤

ወደ እናንተ ስመጣ እነሆ ይህ ሦስተኛዬ ነው ፥ ነገር ፩
ሁሉ በሁለት በሦስት ምስክር የሚፀና አይደለምን?።
ዘዳ ፲፱ ፥ ፲፭ ።
ጥንቱን አስቀድሜ ተናግሬአለሁ ፥ አሁንም አስቀ ፪
ድሜ እናገራለሁ ፥ ቀድሞ ከእናንተ ጋር ሳለሁ እንደ
ነገርኳችሁ እንዲሁ ሦስተኛ ሳልኖርም ቀድሞ በድ
ለው የነበሩትን ለሌሎችም ቢሆን በመጣሁ ጊዜ
ዳግመኛ እንዳልራራ ለሦስተኛ ጊዜ እናገራለሁ ።
በእኔ አድሮ የሚያስተምር የክርስቶስን መከራ ትሽ ፫
ላችሁና ፥ እሱ በእናንተ ዘንድ የሚቻለው ነው እንጂ
ሁሉ የሚሳነው የለም ።
ደክሞ የታመመ የተሰቀለ እርሱ በእግዚአብሔር ፬
ኃይል ሕያው ነውና ፥ እኛም ስለ እናንተ አብረነው
እንደክማለን ፥ በእግዚአብሔር ኃይልም አብረነው
እንነሣለን ። ፊልጵ ፪ ፥ ፯ - ፰ ።
በሃይማኖት እንዳላችሁ ራሳችሁን መርምሩ ፥ ክርስ ፭
ቶስ ከእናንተ ጋር እንዳለ ራሳችሁ አታውቁ አት
ረዱ እንደሆነ ራሳችሁን መርምሩ ፥ እንዲህ ካልሆነ
ግን እናንተ የተናቃችሁ ናችሁ ። ፩ ቆሮ ፲፩ ፥ ፳፰ ።

## ኀበ ሰብአ ቆሮንቶስ ፪ ።

፮ ወእትአመን አንሰ ታእምሩ ከመ ኢኮነ ምኑናነ ንሕነ ።
፯ ወንጼሊ ኀበ እግዚአብሔር ከመ ኢይግበር እኩየ ላዕሌክሙ ወኢ.ምንትኒ ወአኮሰ ከመ ኅሩያነ ንኩን አላ ዳእሙ ከመ አንትሙ ሠናየ ትግበሩ ወንሕነሰ ከመ ምኑናን ።
፰ እስመ ኢንክል ወኢአ እምጽድቅ ዘእንበለ ዳእሙ በጽድቅ ።
፱ ወእትፌሣሕ ሶበ ንሕነ ነሐምም ከመ አንትሙ ትጽንዑ ወትትፌሥሑ ወዝ ውእቱ ጸሎትነ ከመ አንትሙ ታርትዑ ልበክሙ ።

፲ በእንተዝ ዘንተ እጽሕፍ ለክሙ እንዘ ኢሀለውኩ ኀቤክሙ ከመ አመ መጻእኩ ምቱረ ኢይግበር በላዕሌክሙ ከመ ዘሥልጣንበ በዘአኮነኒ እግዚአብሔር ለሐኒፅ ወአኮ ለነሢት ።

፲፩ ተፈሥሑ እንከሰ አኀዊነ አጥብዑ ወተዐገሡ ወተሰነአዉ ወአምላክ ሰላም ወፍቅር የሀሉ ምስሌክሙ።

፲፪ ተአምኁ በበይናቲክሙ በአምኃ ቅድሳት ፣ አምኁክሙ ኵሎሙ ቅዱሳን ።

፲፫ ጸጋሁ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወፍቅረ እግዚአብሔር ወሱታፌ መንፈስ ቅዱስ የሃሉ ምስለ ኵልክሙ አሜን ።

ተፈጸመት መልእክት ዳግሚት ኀበ ሰብአ ቆሮንቶስ ወተጽሕፈት በፊልጵስዩስ ዘመቄዶንያ ወተፈነወት በእደ ቲቶ ወሉቃስ ።

ወስብሐት ለእግዚአብሔር አሜን ።

## ወደ ቆሮንቶስ ሰዎች ፪ ።

እኛም ብንሆን የተናቅን እንዳይደለን ልታውቁ እኔ ፮
አምናለሁ ።
ምንም ክፉ ነገር እንዳያደርጓችሁ ወደ እግዚአብሔር ፯
እንጸልያለን ፣ እኛ የከበርን ልንሆን አይደለም እና
ንተ መልካም ነገር እንድታደርጉ ብቻ ነው እንጂ ፣
እኛ ግን እንደተናቁ ሰዎች ነን ።
በእውነት ፀንተን እንኖራለን እንጂ ፣ ከእውነት መው ፰
ጣት አንችልምና ።
እኛ መከራ በምንቀበልበት ጊዜ ደስ ይለኛል ፣ እና ፱
ንተም ደስ ብሏችሁ በሃይማኖት ትፀኑ ዘንድ ጸሎ
ታችን ይህ ነው ፣ እናንተ ልቡናችሁን ቀና ታደርጉ
ዘንድ ።
ስለዚህም ከእናንተ ዘንድ ሳልኖር ይህን ጻፍኩላ ፲
ችሁ ፣ ለማፍረስ ያይደለ ለማነፅ እግዚአብሔር በሾ
መኝ ገንዘብ ሥልጣን ያለኝ እንደ መሆኔ መጠን በመ
ጣሁ ጊዜ ቍርጥ ነገር እንዳላደርግባችሁ ። ምዕ፡ ፲
፰ ። ምዕ፡ ፲ ፲፩ ።
ወንድሞቻችን! እንግዲህስ ደስ ይበላችሁ ፣ ፅኑ ታገሡ ፲፩
አንድ ሁኑ ፣ የሰላምና የፍቅር አምላክ ከእናንተ ጋር
ይኑር ። ፊል ፬ ፣ ፬ ። ሮሜ ፫ ፣ ፴፫ ።
ክብር ባላት ሰላምታ እርስ በርሳችሁ ሰላም ተባባሉ ፲፪
ቅዱሳን ሁሉ እንዴት ናችሁ ብለዋችኋል ። ፩ ቆሮ
፲፯ ፣ ፳ ።
የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ጸጋ ፣ የእግዚአብሔር ፲፫
አብ ፍቅር የመንፈስ ቅዱስ አንድነት ከሁላችሁ ጋር
ይሁን ። አሜን ።

የመቄዶንያ ክፍል በምትሆን በፊልጵስዩስ ተጽፋ በቲቶና በሉቃስ እጅ ወደ ቆሮንቶስ ሰዎች የተላከችው ሁለተኛይቱ መልእክት ተፈጸመች ።

ለእግዚአብሔር ምስጋና ይሁን ፣ አሜን ።



## ኀበ ሰብአ ገላትያ ፩።



### ምዕራፍ ፩ ።

**ክፍል ፩፣ በእንተ ዘከመ ተሠይመ ጳውሎስ በፈቃደ እግዚአብሔር ።**

፩ እምጳውሎስ ሐዋርያ ዘኢኮነ በእንተ ሰብእ ወኢ
ኮነ እምኀበ ሰብእ ዘእንበለ በእግዚእነ ኢየሱስ ክር
ስቶስ ወእግዚአብሔር አብ ዘአንሥኦ እሙታን ።

፪ ወእምኵሎሙ አኀዊነ እለ ምስሌየ ለቤተ ክርስ
ቲያን ዘገላትያ ።
፫ ሰላም ለክሙ ወጸጋ እግዚአብሔር አቡነ ወእግዚእነ
ኢየሱስ ክርስቶስ ።
፬ ዘመጠወ ርእሶ በእንተ ኃጢአትነ ከመ ያድኅነነ
እምዝንቱ ዓለም ዘይትቃወም በእኩይ በፈቃደ
እግዚአብሔር አቡነ ።
፭ ዘሎቱ ስብሐት ወኃይል ለዓለመ ዓለም አሜን ።
፮ አንከርኩሙ እፎ ከመዝ ፍጡነ ያፈልሱክሙ እምሃ
ይማኖተ ክርስቶስ ዘጸውዐክሙ በጸጋሁ ውስተ
ካልእ ትምህርት ።
፯ ዘኢኮነ ሀልወ ዘእንበለ ዘየሀውኩክሙ ወይፈቅዱ
ይዕልዉ ትምህርቶ ለክርስቶስ ።
፰ ወባሕቱ አንትሙ አሠረ ዚአነ ትልዉ አንትሙሰ
መልአክ እምሰማይ ለእመ መሀረክሙ ካልአ እም
ዘመሀርናክሙ ውጉዘ ለይኩን ።
፱ በከመ እቤ ቀዳሚ ወይእዜኒ ካዕበ እብል ለእመበ
ዘመሀረክሙ ካልአ እምዘመሀርናክሙ ውጉዘ
ለይኩን ።
፲ ወይእዜሰ ለሰብእኑ ንአምን ወእኮ ለእግዚአብሔር
ወእመሰኬ እፈቅድ ለሰብእ አድሎ ኢኮንኩኬ ገብሮ
ለክርስቶስ ።
፲፩ እነግረክሙ አኀዊነ እስመ ትምህርት ዘመሀርኩ
ክሙ ኢኮነ በእንተ ሰብእ ።
፲፪ ወአነሂ አኮ እምኀበ ሰብእ ዘነሣእክዎ ወኢሂ መሀ
ሩኒዮ በዘከሠተ ሊተ እግዚእየ ኢየሱስ ክርስቶስ ።

፲፫ ወሰማዕክሙ ግእዝየ ዘትካት ዘአመ ሀሎኩ ውስተ
አይሁድ ከመ ፈድፋደ ሰደድኩ ቤተ ክርስቲያኑ
ለእግዚአብሔር ወአመንዘዝክዎሙ ።
፲፬ ወከበርኩ በውስተ አይሁድ ፈድፋደ እምኵሉ
ቢጽየ በውስተ ሕዝብየ እስመ ፈድፋደ ኮንኩ
ቀናኤ ለሕገ አበውየ ።
፲፭ ወአመ ሠምረ ወፈቀደ እግዚአብሔር ዘፈለጠኒ አው
ዕአኒ እምከርሠ እምየ ወጸውዐኒ በጸጋሁ ።
፲፮ ወከሠተ ሊተ ወልዶ ከመ ይትዐወቅ ስብሐተ ወ
ልዱ በእዴየ ከመ እስብክ ለአሕዛብ በስሙ ወኢተ
ለውኩ ሰቤሃ ዘሥጋ ወደም ።
፲፯ ወኢዐረጉ ኢየሩሳሌም ኀበ ሐዋርያት ቀደምትየ

## ወደ ገላትያ ሰዎች ፩።

### ምዕራፍ ፩ ።

**ክፍል ፩፣ ጳውሎስ በእግዚአብሔር ፈቃድ ስለ መሾሙ ።**

በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ከሙታን ለይቶ በስነ ፩
ሣው በእግዚአብሔር አብ እንጂ ከሰው ዘንድ ካልተ
ሾመ ስለ ሰው ካልተሾመ ከሐዋርያ ጳውሎስ ቆላ ፲፩
፲፪ ። ግብ ሐዋ ፫ ፲፭ ።
ከኔ ጋር ካሉ ከወንድሞቻችንም ሁሉ የተላከ፣ በገላ ፪
ትያ ላሉችው ቤተ ክርስቲያን ትድረስ ።
ሰላም ለእናንተ ይሁን የአባታችን የእግዚአብሔር ፫
የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስም ጸጋ ይሁንላችሁ ።
በክፉ ግብር ከሚቃወም ከዚህ ዓለም በአባታችን ፬
በእግዚአብሔር ፈቃድ ያድነን ዘንድ ስለ ኃጢአታ
ችን ራሱን አሳልፎ የሰጠን ምዕ ፪ ፳። ፩ ጢሞ ፪ ፮።
ጌትነት ኃይል ለዘለዓለሙ ገንዘቡ የሚሆን አሜን ። ፭
በቸርነቱ የጠራችሁ ክርስቶስን ከማመን አውጥ ፮
ተው ወደ ሌላ ትምህርት እንዲህ ፈጥነው ወሰዱ
አችሁ ብዬ? አደንቃችኋለሁ ።
ያውኳችኋል የክርስቶስንም ወንጌል ሊለውጡ ይወ ፯
ዳሉ እንጂ ቀዋሚ ወደ አይደለ ። ግ፣ ሐ፣ ፲፭ ፩-፳፬።
እናንተ ግን የእኛን ፍለጋ ተከተሉ እናንተስ መል ፰
አክ ከሰማይ ወርዶ እኛ ካስተማርናችሁ ሌላ ቢያስ
ተምራችሁ ውጉዝ ይሁን። ፩ ቆሮ ፲፮ ፳፪ ።
አስቀድሜ እንደተናገርኩ አሁንም ደግሞ ካስተማ ፱
ርናችሁ ትምህርት ሌላ ያስተማራችሁ ቢኖር ውጉ
ዝ ይሁን ። ዘዳግ፣ ፬ ፪ ። ራእ፣ ዮሐ፣ ፳፪ ፲፰ ።
አሁንም ለእግዚአብሔር ያይደለ ለሰው ብለን እና ፲
ምናለን ለሰው የማደላ ከሆንኩስ የክርስቶስ ተገዢ
አይደለሁማ ! ። ፩ ተሰሎ ፪ ፬ ።
ወንድሞቻችን! ልገንራችሁ ያስተማርኳችሁ ትም ፲፩
ህርት ስለ ሰው አይደለም ። ፩ ቆሮ ፲፭ ፩-፫ ።
እኔም ያገኘሁት ከሰው አይደለም ሰዎችም አላስተ ፲፪
ማሩኝም ጌታዬ ኢየሱስ ክርስቶስ በገለጠልኝ ነው
እንጂ ። ፩ ቆሮ ፲፩ ፳፫ ።
በአይሁድ መካከል በነበርኩ ጊዜ የእግዚአብሔርን ፲፫
ማኅበር እጅግ እንደ አሳደድኩ መከራም እንደ አፀና
ሁባቸው የቀድሞ ግብሬን ሰምታችኋል ። ግ ሐ ፳፮ ፱
በአይሁድ ዘንድ ከጓደኞቼ ሁሉ ይልቅ እጅግ ከበ ፲፬
ርኩ በወገኖቼ ዘንድ ለአባቶቼ ሕግ እጅግ ቀናተኛ
ነበርኩና ። ፊል፣ ፫ ፮ ።
የመረጠኝ እግዚአብሔር በወደደ ጊዜ ከእናቴ ማኅ ፲፭
ፀን አውጥቶ በጸጋው ጠራኝ። ሮሜ ፩ ፩ ኤር ፩ ፭።
የልጁ ጌትነት በቃሌ ይገለጥ ዘንድ በስሙ ለአሕዛብ ፲፮
እንዳስተምር እግዚአብሔር ልጁን ገለጠልኝ ያን ጊዜ
ሥጋዊ ደማዊ ሰውን አልተከተልኩም ማቴ ፲፮ ፲፯።
ወደ ቀደሙኝ ወደ ሐዋርያትም ወደ ኢየሩሳሌም ፲፯

ወሐርኩ ብሔረ ዐረብ ወከዕበ ተመየጥኩ ደማስቆ ።

፲፰ ወእምድኅረ ሠለስቱ ዓመት ዐረጉ ኢየሩሳሌም እር
አዮ ለኬፋ ወነበርኩ ኀቤሁ ዐሠረ ወኃሙሰ
መዋዕለ ።
፲፱ ወኢየአምር ባዕደ ሐዋርያተ ዘእንበለ ያዕቆብ
እኁሁ ለእግዚእነ ።
፳ ወዘኒ ዘጸሐፍኩ ለክሙ ናሁ ቅድመ እግዚአብሔር
ሀሎኩ ወኢይኄሱ ።
፳፩ ወእምድኅረዝ በጻሕኩ ደወለ ቂልቅያ ወሶርያ ።

፳፪ ወኢያእመሩኒ አብያተ ክርስቲያናት ዘብሔረ ይሁዳ
እለ በክርስቶስ በገጽየ ።
፳፫ ወዳእሙ ሰምዑ ዜናየ ዝኩአ ዘትካት ይሰድድ
ይእዜ ይሰብክ ትምህርተ ሃይማኖት ።
፳፬ ወይሴብሕዎ ለእግዚአብሔር በእንቲአየ ።

ምዕራፍ ፪ ።

## ክፍል ፪ ፡ በእንተ ግዝረት ወኢተገዝሮ ።

፩ ወእምድኅረ ዐሠርቱ ወአርባዕቱ ዓመት ዓረጉ ካዕበ
ኢየሩሳሌም ምስለ በርናባስ ወነሣእክዎ ለቲቶ ።

፪ ወዐረጉ በዘአስተርአየኒ ወነገርክዎሙ ዘከመ መሀ
ርኩ ወሰበኩ ለአሕዛብ ባሕቲትየ ለእለ ይትሔዘ
ቡኒ ከመ ለከንቱ አረውፅ ወአትባደር ።

፫ ወቲቶሰ ዘምስሌየ እንዘ አረማዊ ውእቱ ኢያገበር
ክዎ ይትገዘር ።
፬ በእንተ ቢጽ ሐሳውያን እለ ተበውኡነ ከመ ያስተ
ሐይጽዋ ለግዕዛንነ ዘረከብነ በኢየሱስ ክርስቶስ ።

፭ ከመ ይቅንዩነ እለ ኢነሐስበሙ ወኢ ከመ ምንትኒ
ኢተቀነይነ ሎሙ ኢሐተሂ ሰዓተ ከመ ይጽናዕ በኀ
ቤክሙ ጽድቀ ትምህርት ።
፮ ወእለሰ ይብሉ መኑ ከማነ እፎ ኮኑ እሙንቱ ትካት
ኢያጽሕቀኒ እንግር እስመ እግዚአብሔር ኢያደሉ
ለገጸ ሰብእ ወእሉሰ በርእሰሙ አልቦ ዘወሰኩኒ
ምንተኒ ።
፯ ዘእንበለ ዳእሙ አእመሩ ከመ ተአመነኒ ትምህርትየ
በኀበ አሕዛብ እለ ኢተገዝሩ በከመ ትምህርቱ ለጴ
ጥሮስ በኀበ አይሁድ እለ ተገዝሩ ።
፰ ወውእቱ ዘአርድኦ ለጴጥሮስ በመልእክቱ ዘመንገለ
ግዝረተ አይሁድ አርድአኒ ሊተኒ ውስተ ቀኖልፈተ
አሕዛብ ።
፱ ወእአሚሮሙ ጸጋሁ ዘወሀበኒ ያዕቆብ ወኬፋ ወዮ
ሐንስ እለ ይብልዎሙ አዕማድ እሙንቱ የማኖሙ
መጠዉኒ ምስለ በርናባስ ከመ ንሳተፍ ምህሮ አሕ

አልወጣሁም ወደ ዐረብ አገር ሄድኩ፥ ዳግመኛም
ወደ ደማስቆ ተመለስኩ ።
ከሦስት ዓመት በኋላ ጴጥሮስን ላየው ወደ ኢየሩሳ ፲፰
ሌም ወጣሁ ከእሱም ዘንድ ዐሥራ አምስት ቀን
ተቀመጥኩ። ግብ ሐዋ ፱ ፳፮ ።
ከጌታችን ወንድም ከያዕቆብ በቀር ከሐዋርያት ሌላ ፲፱
አላውቅም ። ማቴ ፲፫ ፶፭ ።
ይህን የጻፍኩላችሁ እነሆ በእግዚአብሔር ፊት ፳
ነኝ አልዋሽም ።
ከዚህም በኋላ ወደ ቂልቅያና ወደ ሶርያ አውራጃ ፳፩
ደረስሁ። ግብ ሐዋ ፱ ፴ ።
በክርስቶስ ያመኑ በይሁዳ አገር ያሉ ማኅበረ ክርስ ፳፪
ቲያን ፊቴን አይተው አላወቁኝም ።
ቀድሞ ምእመናንን ያሳድድ የነበረው ያ ዛሬ የሃይማኖ ፳፫
ትን ትምህርት ይሰብካል ሲባል ወሬዩን ሰሙ እንጂ ።
በእኔ ምክንያትም እግዚአብሔርን ያመሰግኑታል ። ፳፬

ምዕራፍ ፪ ።

## ክፍል ፪ ፡ ስለ መገዘርና አለመገዘር ።

ከዐሥራ አራት ዓመትም በኋላ ከበርናባስ ጋር እንደ ፩
ገና ወደ ኢየሩሳሌም ወጣሁ ቲቶንም ይዤው ሄድ
ኩ። ግብ ሐዋ ፲፭ ፪ ።
በታየኝ ራእይ ምክንያት ወጣሁ ለከንቱ እንደምሮጥ ፪
እንደምቀዳደም አድርገው ለሚጠራጠሩኝ ሰዎች
ለአሕዛብ ብቻዬን ወንጌልን እንደ አስተማርኩ ነገር
ኳቸው። ቆሮ ፮ ፱ ።
አብሮኝ የነበረው ቲቶ ግን አረማዊ ሲሆን ግድ ተገ ፫
ዘር አላልኩትም ። ግብ ሐዋ ፲፮ ፫ ።
በኢየሱስ ክርስቶስ ያገኘናትን ነፃነት ለመንቀፍ ፬
ጣልቃ የገቡብንም አሰተኞች ሰባኪዎችን ደስ እን
ዳይላቸው ብዬ። ግብ ሐዋ ፲፭ ፳፬ ።
ይገዙናል ብለን የማናስባቸው አንዲት ሰዓት እንኳን ፭
በምንም በምን ያልተዋረድንላቸው የወንጌል
እውነትነት በእናንተ ይፀና ዘንድ። ምዕ ፫ ፩ ።
ማነው እንደኛ የሚሉ ግን ቀድሞ እነሱ ምን እንደ ፮
ነበሩ ልናገር አያሳስበኝም እግዚአብሔር የሰው
ፊት አይቶ አያደላምና እነሱ ግን በሥልጣናቸው
ምንም የጨመሩልኝ ነገር የለም። ግብ ሐዋ ፲ ፴፬ ።
ግን የጴጥሮስ ትምህርት በተገዘሩ በአይሁድ እንደ ፯
ታመነለት የእኔም ትምህርቴ ባልተገዘሩ በአሕዛብ
ዘንድ እንደታመነልኝ አወቁ። ግብ ሐዋ ፲፫ ፵፯ ።
ወደ ተገዘሩ አይሁድ በተላከ ጊዜ ጴጥሮስን የረዳው ፰
እርሱ እኔንም ባልተገዘሩ አሕዛብ ዘንድ ረዳኝ ።

አዕማድ ናቸው የሚሏቸው ያዕቆብ ኬፋና ዮሐንስ ፱
የሰጠኝን ጸጋ አውቀው ከበርናባስ ጋር ቀኝ እጃቸ
ውን ሰጡኝ፥ እነሱ አሕዛብን በማስተማር እንድንተ

ዘብ ወእሙንቱ ይሑሩ ኀበ አይሁድ፣ ወንሕነኒ
ኀበ አረሚ ።
፲ ዳእሙ ከመ ንዘከሮሙ ለነዳያን ወበእንተዝ ጽሕቁ
እግበሮ ለዝንቱ ።
፲፩ ወአመ መጽአ ኬፋ አንጾኪያ ተቃወምክዎ ወግዕ
ዝክዎ ቅድመ ገጹ ።
፲፪ እስመ ዘእንበለ ይምጽኡ እደው እምኀበ ያዕቆብ
በልዐ ምስለ አረሚ፣ ወአመ መጽኡ ተግኅሦሙ
እስመ ፈርሆሙ ለእለ እምአይሁድ ።
፲፫ ወበዝንቱ እለ ገብኡ ኀበ ዝንቱ ግብር እምአይሁድ
ወበርናባስኒ ኀብረ ምስሌሆሙ ወአድለወ ሎሙ ።
፲፬ ወሰበ ርኢኩ ከመ ኢያርትዑ እግሮሙ ኀበ ጽድቀ
ትምህርት እቤሎ ለኬፋ በቅድመ ኵሎሙ ሰበ አንተ
እንዘ አይሁዳዊ አንተ በሕገ አረሚ ትነብር ወአኮ
በሕገ አይሁድ እፎ እንከ ታጌብሮሙ ለአረሚ
ይትየሀዱ ።
፲፭ ወእንዘ ንሕነ እለ ፍጥረትነ እምአይሁድ ወአኮ
እምአሕዛብ ኃጥአን ።
፲፮ እስመ ነአምር ከመ ኢይጸድቅ ሰብአ በገቢረ ሕገገ
ኦሪት ዘእንበለ ዳእሙ በአሚን በኢየሱስ ክርስቶስ
ወንሕነኒ አመነ በኢየሱስ ክርስቶስ ወበሃይማኖትነ
ቦቱ ንጸድቅ ወአኮ በገቢረ ሕገገ ኦሪት እስመ በገ
ቢረ ሕገገ ኦሪት ኢይጸድቅ ኵሉ ዘነፍስ ።

፲፯ ወእመሰ እለ ንፈቅድ ንጽደቅ በክርስቶስ ኮነ ከመ
ኃጥአን ክርስቶስ እንከ ላእከ ኃጢአትኑ እንጋ ሐሰ።

፲፰ ወእመሰኬ ዝኰ ዘነሠትኩ ኪያሁ ከመ አሐንፅ
ዐላዌ ረሰይኩ ርእስየ ።
፲፱ አንሰኬ እምሕግ ዘቀዳሚ ሞትኩ ከመ እሕየው
በካልእ ሕግ ለእግዚአብሔር ።
፳ ወተሰቀልኩ ምስለ ክርስቶስ፣ ሕይወትየሰ ኀልቀት
ወበሕይወተ ክርስቶስ ሀለውኩ ወዘኒ ዘአሐዩ ይእዜ
በሥጋየ በአሚን በወልደ እግዚአብሔር አሐዩ
ዘአፍቀረኒ ወመጠወ ርእሶ በእንቲአየ ።

፳፩ ወኢይክሕድ ጸጋ እግዚአብሔር፣ እመሰኬ በገቢረ
ሕገገ ኦሪት ይጸድቁ ለከንቱኬ ሞተ ክርስቶስ ።

ምዕራፍ ፫ ፤

<u>ክፍል ፫፣ ዘከመ ጸድቀ አብርሃም በሃይማኖት ።</u>

፩ ኦ አብዳን ሰብአ ገላትያ መኑ አሕመመክሙ ከመ
ኢትእመኑ በጽድቅ ዘያስተርኢ ለዓይን ኢየሱስ
ክርስቶስ ዘአቅድመ ተጽሕፎ በእንቲአሁ ከመዪ
ይሰቀል ።

በበር እነሱ ወደ አይሁድ ሊሄዱ፣ እኛ ወደ አረማ
ውያን ልንሄድ። ዮሐ ፩ ፵፪ ።
ግን ነዳያንን እንድናስበቸው ነገሩኝ ስለዚህም ይህን ፲
ነገር ልፈጽመው ወደድኩ። ግብ ሐዋ ፲፩ ፴። ፲፪ ፳፪።
ኬፋ ወደ አንጾኪያ በመጣ ጊዜ ፊት ለፊት ተቃወ ፲፩
ምኩት ነቀፍኩትም ።
ሰዎች ከያዕቆብ ዘንድ ሳይመጡ ከአረማውያን ጋር ፲፪
ሲበላ ቈይቶ ከአይሁድ ወገን የሆኑትን ስለ ፈራ እነሱ
በመጡ ጊዜ ተለይቷቸዋልና። ግብ ሐዋ ፲፩ ፫ ።
ከአይሁድ ወገን ወደዚህ ግብር የተመለሱ ብዙ ነበሩ ፲፫
በርናባስም እንኳ ከነርሱ ተባብሮ ለነሱ አደላ ።
እግራቸውን ወደ ወንጌል እውነትነት እንዳላቀኑ በየሁ ፲፬
ጊዜ በሰው ሁሉ ፊት ጴጥሮስን እንዲህ አልኩት፣
አንተ አይሁዳዊ ስትሆን በአይሁድ ሕግ ያይደለ በአ
ረማውያን ሕግ የምትኖር ሲሆን አረማውያንን አይ
ሁድ እንዲሆኑ ለምን ታስገድዳቸዋለህ? ብዬ ።
ከአሕዛብ ሳይሆን ከአይሁድ የተወለድን እኛ አይ ፲፭
ሁድነት የሌለን ስንሆን ።
ሰው በኢየሱስ ክርስቶስ በማመን እንጂ የኦሪትን ፲፮
ሕግ በመፈጸም እንደማይጸድቅ እናውቃለንና እኛም
በኢየሱስ ክርስቶስ አምነናል የኦሪትን ሕግ በመፈ
ጸም ያይደለ እሱን በማመናችን እንከብራለን፣ ሰው
ሁሉ የኦሪትን ሕገጋት በመፈጸም አይጸድቅምና።
ግብ ሐዋ ፲፭ ፲ - ፲፩ ። ሮሜ ፫ ፳ - ፳፰ ።
በክርስቶስ ልንከብር የምንሻ እኛ እንደ ኃጢአተ ፲፯
ኞች ከሆነ እንግዲህ ክርስቶስ የኃጢአት አገልጋይ
መሆኑ ነዋ? አይደለም ።
ያን ያፈረስኩትን መልሼ የምሠራው ከሆንኩማ ፲፰
ራሴን ትእዛዝ አፍራሽ አደረግሁ ።
እኔስ ከፊተኛው ሕግ ተለይቻለሁ፣ እግዚአብሔርን ፲፱
ለማገልገል በሌላው ሕግ እኖር ዘንድ። ሮሜ ፯ ፮።
ከክርስቶስ ጋር ተሰቅያለሁ ሕይወቴ ግን አልፋለች፣ ፳
በክርስቶስ ሕይወትነት አለሁ ዛሬ በሥጋዬ የምኖ
ረው ሕይወትም የእግዚአብሔርን ልጅ በማመን
እኖራለሁ፣ የወደደኝን ስለ እኔም ራሱን አሳልፎ
የሰጠልኝን። ዮሐ ፲፮ ፳፫ ። ምዕ ፩ ፬ ።
የእግዚአብሔርን ጸጋ አልክድም፣ የኦሪትን ሕግ ፳፩
በመሥራት የሚጸድቁ ከሆነ ክርስቶስ በከንቱ
ሙቷላ! ።

ምዕራፍ ፫ ።

<u>ክፍል ፫፣ አብርሃም በሃይማኖት እንደከበረ ።</u>

እናንተ ሰነፎች የገላትያ ሰዎች! ለዓይን በሚታየው ፩
እውነት እንዳታምኑ ማን አታለላችሁ? ይኸውም
እንዲሰቀል አስቀድሞ ስለርሱ የተጻፈለት ኢየ
ሱስ ክርስቶስ ነው ።

፪ ዘንተ ዳእሙ እፈቅድ አእምር በኀቤክሙ በገቢረ
ሕገገ ኦሪትኑ ዘነሣእክሙ መንፈሰ ቅዱሰ አው በሰ
ሚዐ ሃይማኖት ።
፫ ከመዝኑ ዓብዳን አንትሙ እምድኅረ ዘመንፈስ
ቅዱስ ወጠንክሙ ወገባእክሙ ይእዜ ሕገ ዘሥጋ
ወደም ትግበሩ ።
፬ ወመጠነዝ ሐሚመክሙ ለከንቱ ረሰይክሙ ።
፭ ውእቱ ዘይሁበክሙ መንፈሰ ወይገብር ለክሙ ኃይለ
በገቢረ ሕገገ ኦሪትኑ አው በሰሚዐ ሃይማኖት ።
፮ በከመ አብርሃም አምነ በእግዚአብሔር ወኮኖ ጽድቀ።
፯ ተእምሩ እንከ ከመ እለ አምኑ ውሉደ አብርሃም
እሙንቱ ።
፰ እስመ አቅደመ አእምሮ መጽሐፍ ከመ በአሚን
ያጸድቆሙ እግዚአብሔር ለአሕዛብ ናሁ አቅደመ
አሰፍዎቶ እግዚአብሔር ለአብርሃም ከመ ቦቱ ይት
ባረኩ ኵሎሙ አሕዛብ ።
፱ ወይእዜሰኬ እለ የአምኑ ይትባረኩ ምስለ አብርሃም
ምእመን ።
፲ ወኵሎሙ እለ ውስተ ሕገ ኦሪት ሀለዉ ውስተ መር
ገም ይነብሩ እስመ ከመዝ ይቤ መጽሐፍ ርጉመ
ለይኩን ኵሉ ዘጽሑፍ ውስተ ዝንቱ መጽሐፈ ኦሪት
ዘኢይፌጽም ገቢሮቶ ።
፲፩ ወእምከመሰ ኢይጸድቁ በገቢረ ሕገገ ኦሪት በኀበ
እግዚአብሔር ይትዐወቅ ከመ በአሚን ይጸድቁ፤
ወጻድቅኒ በአሚን የሐዩ በከመ ጽሑፍ ።
፲፪ ኦሪትሰ ኢኮነ በአሚን ዘያጸድቅ ዳእሙ ዘፈጸመ
ገቢሮቶ የሐዩ ቦቱ ።
፲፫ ወለነሰ ተሣየጠነ ክርስቶስ እመርገማ ለኦሪት በዘወ
ድአ በእንቲአነ ወፆረ መርገማ እስመ ከመዝ ይቤ
መጽሐፍ ርጉም ውእቱ ኵሉ ዘስቁል ዲበ ዕፅ ።
፲፬ ከመ ይግባእ በረከተ አብርሃም ላዕለ አሕዛብ በእ
ንተ ኢየሱስ ክርስቶስ ወንርከብ ተስፋሁ ለመንፈስ
ቅዱስ በአሚን በክርስቶስ ።

<u>ክፍል ፬፡ በእንተ ኪዳን ዕኑዕ ።</u>

፲፭ ሕገ ሰብእ ንብል ሰብእ ጥቀ ኢየዐቢ ወኢይትከሐድ
ኪዳነ ዘዕኑዕ ።
፲፮ ወለአብርሃምኒ አሰፈዎ እግዚአብሔር ወይቤሎ ለከ
ወለዘርእከ ወኢይቤሎ ለከ ወለአዝርእቲከ ከመ ዘለ
ብዙኃን ዘእንበለ ከመ ዘለአሐዱ ለዘርእከ ዘውእቱ
ክርስቶስ ።
፲፯ እብል እንከ ዝንቱ ኪዳን ጽኑዕ ዘአምኀበ እግዚአብ

ከናንተ ዘንድ ይህን ብቻ ልታውቁ እወዳለሁ መን ፪
ፈስ ቅዱስን የተቀበላችሁ የኦሪትን ሕግ በመፈጸም
ነውን? ወይስ ሃይማኖትን በመስማት? ።
መንፈሳዊ ሥራን ከጀመራችሁ በኋላ ሥጋዊ ደማዊ ፫
ሥራ ልትሠሩ ተመለሳችሁ፤ እንዲህን ሰነፎች
ናችሁን? ።
ይህን ያህል መከራ ተቀብላችሁ ለከንቱ አደረጋ ፬
ችሁት ።
እርሱ መንፈስ ቅዱስን የሚሰጣችሁ ተአምራት ፭
የሚያደርግላችሁ የኦሪትን ሕግ በመፈጸም ነውን?
ወይስ ሃይማኖትን በመማር? ።
አብርሃም በእግዚአብሔር እንዳመነ ጽድቅም ፮
ሆኖ እንደ ተቈጠረለት ። ዘፍጥ፡ ፲፭ ፮ ።
እንግዲህ ያመኑ የአብርሃም ልጆች እንደሆኑ ታው ፯
ቃላችሁ ።
እግዚአብሔር አሕዛብን በሃይማኖት እንደሚያጸድ ፰
ቃቸው መጽሐፍ አስቀድሞ ገልጧልና፤ አሕዛብ
ሁሉ በእሱ እንዲባረኩ እነሆ እግዚአብሔር አስቀ
ድሞ ለአብርሃም ተስፋ ሰጠው ። ዘፍ፡ ፲፪ ፫ ።
አሁንም የሚያምኑ ከታማኙ ከአብርሃም ጋር ይባ ፱
ረካሉ ። ሮሜ ፱ ፲፮ ።
በኦሪት ሕግ ያሉ ሁሉ በመርገም ውስጥ ይኖራሉ ፲
በኦሪት ውስጥ የተጻፈውን ሠርቶ ያልፈጸመ ሁሉ
መጽሐፍ ርጉም ይሁን ብሏልና ። ዘዳ፡ ፳፮ ፳፮ ።
በእግዚአብሔር ዘንድ የኦሪትን ሕግ በመሥራት ፲፩
የማይጸድቁ ከሆነማ በሃይማኖት እንደሚከብሩ ይታ
ወቃል እንደተጻፈውም ጻድቅ በሃይማኖት ይድ
ናል ። እንባ ፪ ፬ ። ሮሜ ፩ ፲፮ ።
ኦሪትስ በሃይማኖት የሚያጸድቅ አይደለም ሠርቶ ፲፪
የፈጸመው ይድንበታል እንጂ ። ዘሌ፡ ፲፰ ፭ ።
እኛንስ ክርስቶስ ስለእኛ ተላልፎ መርገሟን በመሸ ፲፫
ከሙ ከኦሪት መርገም ዋጅቶናል መጽሐፍ እንዲህ
ብሏልና "በዕንጨት ላይ የተሰቀለ ሁሉ ርጉም ነው" ።
ሮሜ ፰ ፫ ። ፪ ቆሮ ፭ ፳፩ ። ዘዳግ፡ ፳፩ ፳፫ ።
በኢየሱስ ክርስቶስ ስላመኑ የአብርሃም በረከት ፲፬
ለአሕዛብ ይሆን ዘንድ እኛም ክርስቶስን በማመን
የመንፈስ ቅዱስን ተስፋ እናገኝ ዘንድ ።

<u>ክፍል ፬፡ ኪዳን ፅኑ ስለ መሆኑ ።</u>

የሰውን ሥርዓት እንናገር ሰው እንኳን ፅኑ ኪዳን ፲፭
ገብቶ አያፈርስም ። ዕብ፡ ፱ ፲፯ ።
እግዚአብሔርም ለአብርሃም ለአንተና ለዘርህ ብሎ ፲፮
ተስፋ ሰጠው፤ ብዙዎች አድርጎ ላንተና ለዘሮችህ
አላለውም ለአንድ እንደሚናገር አድርጎ ለዘርህ
አለው እንጂ ይኸውም ክርስቶስ ነው ። ዘፍ ፳፪ ፲፰ ።
እንግዲህ ይህ ከእግዚአብሔር የተሰጠ ፅኑ ኪዳን ፲፯

ሔር ወእምድኅሬሁ በአርበዕቱ ምእት ወሠላሳ ክረ
ምት መጽአት ኦሪት ወአኮሰ ከመ ትክላእ ዘአሰፈዎ
እግዚአብሔር ።
፲፰ ወእመሰኬ በገቢረ ሕገገ ኦሪት ይወርሱ ኢኮነኬ በዘ
አሰፈዎ ናሁ አቅደመ አሰፍዎቶ እግዚአብሔር ለአ
ብርሃም ።
፲፱ ለምንት እንከ መጽአት ኦሪት ከመ ታብዝኃ ለኃጢ
አት እስከ አመ ይበጽሕ ዝኩ ዘርእ ዘሎቱ አሰፈወ
ወወረደት ሥርዓት ምስለ መላእክት በእደ ኀሩይ ።

፳ ወኀሩይሰ ኢኮነ ለአሐዱ ዘእንበለ አሐዱ እግዚአ
ብሔር ውእቱ ።
፳፩ ኦሪት እንከ ትክላእኑ ዘአሰፈወ እግዚአብሔር መጽ
አት ሐሰ ሶበሁ ተውህበ ሕግ ዘይክል አሕይዎ በው
እቱ ሕግ እምኮነ ጽድቅ ።

፳፪ ወባሕቱ ዘግሐ መጽሐፍ ለኵሉ ውስተ ኃጢአት
ከመ ይኩን ተስፋ በአሚን በኢየሱስ ክርስቶስ ወይ
ርከብዎ እለ የአምኑ ።
፳፫ ወዘእንበለ ይብጻሕ አሚን አቀበተነ ኦሪት ወመርሐ
ተነ ውስተ አሚን ዘይመጽእ ።
፳፬ ኦሪት እንከ መርሐ ኮነተነ ለኀበ ክርስቶስ ከመ ንጽ
ደቅ በአሚን ቦቱ ።
፳፭ ወሶበ መጽአት እንከ አሚን ኢንፈቅድ እንከ መርሐ ።
፳፮ እስመ ኵልነ ውሉደ እግዚአብሔር ንሕነ በአሚን
በኢየሱስ ክርስቶስ ።
፳፯ ወአንትሙሰ እለ ተጠመቅሙ በክርስቶስ ፡ ክርስቶ
ስሃ ለበስክሙ ።
፳፰ አልቦ በዝንቱ አይሁዳዊ ወአልቦ አረማዊ ወአልቦ
ነባሪ አልቦ አግዓዚ አልቦ ተባዕት ወአልቦ አንስት
ዳእሙ ኵልክሙ አሐዱ በኢየሱስ ክርስቶስ ።
፳፱ ወእምከመ ኮንክሙ ለኢየሱስ ክርስቶስ አንትሙኬ
እንከ ዘርአ አብርሃም ወራስያነ ተስፋ ።

ምዕራፍ ፬ ፤

<u>ክፍል ፩፡ ዘከመ ተወልደ እግዚእነ እማርያም።</u>

፩ ወባሕቱ እብል አምጣነ ሕፃን ውእቱ ወራሲ አልቦ
ዘይኄይስ እምነባሪ እንዘ እግዚእ ውእቱ ለኵሉ ።
፪ ወባሕቱ ላዕለ እምሔው ወላዕለ መገብት ይትዐቀብ
እስከ ይበጽሕ ዕድሜሁ ዘአደሞ አቡሁ ።
፫ ከማሁ ንሕነኒ አመ ሕፃናት ንሕነ ተቀነይነ ለስሒተ
ዝንቱ ዓለም ።
፬ ወአመ በጽሐ ዕድሜሁ ፈነወ እግዚአብሔር ወልዶ
ወተወልደ እምብእሲት ወገብረ በሕገ ኦሪት ።
፭ ከመ ይሣየጦሙ ለእለ ውስተ ኦሪት ከመ ንርከብ
ትርሲተ ውሉድ ።

ነው እላለሁ ከዚህ በኋላ በአራት መቶ ሠላሳ ዓመት
ኦሪት ተሠራች ግን እግዚአብሔር የሰጠውን ተስፋ
ልትከለክል አይደለም ። ዘፀ፡ ፲፪ ፵ ።
የኦሪትን ሕግ በመሥራት ተስፋውን የሚወርሱ ፲፰
ከሆነ እንግዲያ በሰጠው ተስፋ አይደለማ እነሆ እግዚ
አብሔር አስቀድሞ ለአብርሃም ተስፋውን ሰጠው ።
ታዲያ ኦሪት ለምን ተሠራች ኃጢአትን ታበዛት ፲፱
ዘንድ ነው? ተስፋ ያደረገለት ያ ዘር እስኪመጣ ድረስ
እንደ መላእክት ሆነው ሊያገለግሉበት በአስታራቂው
እጅ ሥርዓት መጣች ። ሮሚ ፭ ፳። ግብ ሐ ፯ ፶፫።
ኅሩይ ግን ከአንድ ከእግዚአብሔር በቀር አንድም ፳
የለም ።
እንግዲህ ኦሪት እግዚአብሔር የሰጠውን ተስፋ ልት ፳፩
ከለክል ተሠራችን ልትከለክል አልተሠራችም ማዳን
የሚቻለው ሕግ ተሠርቶ ቢሆንማ ኖሮ በዚያ ሕግ
ጽድቅ በተገኘ ነበር ። ሮሚ ፰ ፪ - ፬ ።
ነገር ግን መጽሐፍ ሁሉንም በኃጢአት በረት ዘግቶ ፳፪
ተወው ፡ ተስፋ ኢየሱስ ክርስቶስን በማመን ይሆን
ዘንድ ያመኑም ያገኙት ዘንድ ። ሮሚ ፫ ፱ - ፲፱ ።
ሃይማኖት ሳይመጣ ኦሪት ጠበቀችን ፡ ወደሚመጣ ፳፫
ውም እምነት መራችን ። ምዕ፡ ፬ ፫ ።
እንግዲህ ኦሪት ወደ ክርስቶስ ለመድረስ መሪ ሆነ ፳፬
ችን እሱን አምነን እንከብር ዘንድ ።
እንግዲህ ሃይማኖት ከመጣች መሪ አንሻም ሮሚ ፲ ፬። ፳፭
ኢየሱስ ክርስቶስን በማመን ሁላችን የእግዚአብሔር ፳፮
ልጆች ሆነናልና ። ዮሐ፡ ፩ ፲፪ ። ሮሚ ፰ ፲፯ ።
በክርስቶስ የተጠመቃችሁ እናንተማ ክርስቶስን ፳፯
ለብሳችኋል ። ሮሚ ፯ ፫ ። ፲፫ ፲፬ ።
በዚህ አይሁዳዊ አረማዊ የለም ፡ገገርም ተገገርም ፳፰
የለም ወንድ ሴት የለም ሁላችሁም በኢየሱስ ክር
ስቶስ አንድ ናችሁ እንጂ ። ሮሚ ፲ ፲፪ ።
ለኢየሱስ ክርስቶስ ልጆች ከሆናችሁም እንግዲህ ፳፱
ተስፋውን የምትወርሱ የአብርሃም ዘሮች እናንተ
ናችሁ ። ቈ፡ ፯ ። ሮሚ ፱ ፯ ።

ምዕራፍ ፬ ።

<u>ክፍል ፩ ፡ ጌታችን ከእመቤታችን እንደተወለደ።</u>

ግን ወራሲው ሕፃን ሳለ ለሁሉ ጌታ ሲሆን ከቤተ ፩
ሰብ የሚሻለው የለም ።
አባቱ የወሰነው ዕድሜው እስኪደርስ ድረስም ከአ ፪
ያት በሞግዚት እጅ ይጠበቃል እንጂ ።
እንዲሁ እኛም ሕፃናተ አእምሮ በነበርነ ጊዜ ለዚህ ፫
ዓለም ስሕተት ተገዝተን ነበር። ምዕ፡ ፫ ፳፫። ፭ ፩ ።
ቀጠሮው በደረሰም ጊዜ እግዚአብሔር ልጁን ላከ ፬
ከሴትም ተወለደ የኦሪትንም ሕግ ፈጸመ። ዳን፡ ፱ ፳፬።
በኦሪት የነበሩትን ይዋጃቸው ዘንድ እኛ የልጅነትን ፭
ክብር እናገኝ ዘንድ ። ምዕ፡ ፫ ፲፫ ።

፮ ወእምከመሰ ውሉድ አንትሙ ናሁ ፈነወ እግዚአብ
ሔር መንፈሰ ወልዱ ውስተ ልብክሙ ውእቱ ዘት
ጼውዖ ወትብሉ አባ ወአቡየ ።
፯ እንከሰኬ ውሉድ አንትሙ ወኢኮንክሙ አግብርተ
ወእመሰኬ ውሉድ አንትሙ ወራስያኒሁኬ ለእግዚ
አብሔር አንትሙ በኢየሱስ ክርስቶስ ።
፰ ወበሕቱ ትካትሰ በኢያእምሮትክሙ ተቀነይክሙ
ለእለ ኢኮኑ አማልክተ ።
፱ ወይእዜሰ አእመርክምዎ ለእግዚአብሔር ወፈድፋደ
ውእቱ አእመረክሙ እፎ ካዕበ ኀበ ዝኩ ድኩም
ወጽኑስ ጣዖተ ዝ ዓለም ትፈቅዱ ፈጠሬ ትትቀነዩ
ሎሙ ።
፲ ወትትዓቀቡ ዕለተ ወወርኀ ወጊዜ ወዓመታተ ።
፲፩ እፈርሀክሙ እንዳዒ ለእመ ለከንቱ ፃመውኩ በእን
ቲአክሙ ፡ ኩኑ ከማየ እስመ አነሂ ከማክሙ ኮንኩ ።

ክፍል ፮ ፡ በእንተ ቅንአት በገቢረ ሠናይ ።

፲፪ አኀዊነ አስተበቍዐክሙ እስመ ኢገፋዕክሙኒ ።
፲፫ ተአምሩ ከመ በአምጣነ ድከመ ኃይልየ መሀርኩ
ክሙ ቀዲሙ ።
፲፬ ወእንዘሂ አሐምም ኢተቈጣዕክሙኒ ወኢመነንክ
ሙኒ በሥጋየ ወተወከፍክሙኒ ከመ መልአከ እግዚ
አብሔር ወከመ ክርስቶስ ኢየሱስ ።
፲፭ አይቴኑ እብዕያትክሙ ይእዜ አነ ሰማዕትክሙ ከመ
ሶበ ይትከሃለክሙ አዕይንቲክሙ መሊሐክሙ እም
ወሀብክሙኒ ።
፲፮ ጸላኤኑ ኮንኩክሙ ሶበ መሀርኩክሙ ጽድቀ ።
፲፯ ወእሉሰ ይቀንኡ ላዕሌክሙ ወአኮ ለሠናይ ዳእሙ
ይዝግሑክሙ ይፈቅዱ ከመ ትቅንኡ ላዕሌሆሙ ።
፲፰ ሠናይኬ ከመ ትቅንኡ ለገቢረ ሠናይ ኵሎ ጊዜ
ወአኮ ዳእሙ በሀልዎ ዚአየ ኀቤክሙ ።
፲፱ ደቂቅየ እለ ዳግመ አሐምም ብክሙ እስከ አመ ያስ
ተርኢ ክርስቶስ ውስተ ልብክሙ ።
፳ ወእፈቅድ አሀሉ ኀቤክሙ ይእዜ ወእዌልጥ ቃልየ
እስመ አኀጥእ ዘእብል በእንቲአክሙ ።

ክፍል ፯ ፡ በእንተ ይስሐቅ ወይስማኤል ፡ ሣራ ወአጋር ።

፳፩ ትብሉኑ በሕገ ኦሪት ነሀሉ ወኢትሰምዕዋኑ ለኦሪት ።
፳፪ እስመ ጽሑፍ ውስቴታ ከመ አብርሃም ክልኤተ
ደቂቀ ወለደ አሐደ እምዕቅብቱ ወአሐደ እምአግ
ዓዚት ።



ልጆች እንደ መሆናችሁ መጠን እግዚአብሔር የል ፮
ጁን መንፈስ በልባችሁ አሳደረ ፡ አባ አባቴ ብላችሁ
የምትጠሩት እርሱ ነው ። ሮሜ ፰ ፲፭።
እንኪያስ እናንተ ልጆች ናችሁ እንጂ ባሮች አይደ ፯
ላችሁም ፡ ልጆች ከሆናችሁም በኢየሱስ ክርስቶስ
የእግዚአብሔር ወራሾች ናችኋ! ምዕ ፫ ፳፱ ።
ቀድሞማ ባለማወቃችሁ አማልክት ላይደሉ ተገ ፰
ዝታችሁ ነበር ።
ዛሬ ግን እግዚአብሔርን አወቃችሁት ፡ ይልቁንም ፱
እሱ አወቃችሁ ፡ እንግዲህ ለዚያ ለደካማው ለድኻው
ለዚህ ዓለም ጣዖት እንደገና ልትገዙ እንዴት
ትሻላችሁ ?
ዕለትን ወርን ጊዜን ዓመታትን ለምን ትጠብቃላ ፲
ችሁ? ሮሜ ፲፬ ፭ ።
ስለ እናንተ በብላሽ ደክሜ እንደሆነ ብዬ እፈራች ፲፩
ኋለሁ ፡ እንደኔ ሁኑ እኔም እንደ እናንተ ሁኜለ
ሁና ። ፪ ዮሐ ቍ ፰ ።

ክፍል ፮፡ ስለ በጎ ሥራ መቅናት ።

ወንድሞቻችን! አልበደላችሁኝምና እማልዳችኋለሁ ፲፪
ባለኝ ድካም መጠን እንደ አስተማርኳችሁ ታውቃ ፲፫
ላችሁ ። ፩ ቆሮ ፪ ፫ ።
መከራ እቀበል በነበረበትም ጊዜ አልሰለቻችሁኝም ፲፬
በሰውነቴም አልናቃችሁኝም እንደ እግዚአብሔር
መልአክ እንደ ኢየሱስ ክርስቶስም ተቀበላችሁኝ።
አሁን ግን ማክበራችሁ ወዴት አለ? ቢቻላችሁስ ፲፭
ዓይኖቻችሁን አውጥታችሁ ልትሰጡኝ ትወዱ እንደ
ነበረ ምስክራችሁ ነኝ ።
እውነቱን ስለ አስተማርኳችሁ ባላጋራ ሆንኳችሁን። ፲፮
አሞ ፡ ፭ ፲ ።
እነዚያማ ይቀኑባችኋል ግን ለመልካም አይደለም ፲፯
በነሱ ላይ እንድትቀኑ ሊያሰናክሏችሁ ይወዳሉ
እንጂ ። ምዕ ፡ ፩ ፯ ።
መቅናትስ ዘወትር ለመልካም ሥራ ልትቀኑ ይገ ፲፰
ባል ፡ ግን እኔ ከእናንተ ዘንድ ባለሁበት ጊዜ ብቻ
አይደለም ።
እንደገና መከራ የምቀበልላችሁ ልጆቼ ክርስቶስ ፲፱
በልባችሁ እስኪሳልባችሁ ድረስ ። ፩ ቆሮ ፬ ፲፭ ።
ቃሌን ለውጬ አሁን ከእናንተ ዘንድ ልገኝ እሻለሁ ፳
ስለ እናንተ የምናገረውን አጣለሁና ።

ክፍል ፯ ፡ ስለ ይስሐቅና ይስማኤል ፡ ስለ ሣራና አጋር ።

በአራት ሕግ እንኑር ትላላችሁን? ኦሪትን አትሰሟ ፳፩
ትምን ? ። ቍ ፱ ፡ ምዕ ፫ ፳፫ ።
አብርሃም ሁለት ልጆች ወለደ አንዱን ከእመቤቲቱ ፳፪
አንዱን ከዕቁባቱ እንደ ወለደ ተጽፎባታልና ።
ዘፍጥ ፡ ፲፮ ፲፭ ። ፳ ፩ ፪ ።

፳፫ ወባሕቱ ክልእ ልደቱ ለዘእምዕቀብቱ ሕገ ሰብእ ተወ
ልደ፣ ወዘሰ እምአግዓዚት በዘአሰፈዎ ።

፳፬ ወዝ ውእቱ አምሳለ ክልኤቱ ሥርዓት ወአሐቲሰ
እምደብረ ሲና ተወልደት ለቅኔ ወይእቲሰ አጋር ።

፳፭ ወሲናሰ ደብር ውእቱ በብሔረ ዓረብ ወትትናፀር
ምስለ ኢየሩሳሌም እንተ በታሕቱ ምድራዊት ወት
ትቀነይ ምስለ ደቂቃ ።
፳፮ ኢየሩሳሌምሰ እንተ ላዕሉ አግዓዚት ይእቲ ወይእቲ
እምነ ።
፳፯ ጽሑፍ ትትፌሣሕ መካን እንተ ኢትወልድ ወትት
ኃሠይ ወትኬልሕ እንተ ኢተአምር ማሕምመ እስመ
ብዙኃ ውሉዳ ለመዓስብ እምእንተ ባቲ ምት ።

፳፰ ወንሕነሰ አኀዊነ ውሉደ ተስፋ አምሳለ ይስሐቅ ።

፳፱ ወበከመ ዘበሕገ ሥጋ ተወልደ ሰደዶ ለዘበመንፈስ
ተወልደ ከማሁ ይእዜኒ ።

፴ ወባሕቱ ምንተ ይቤ መጽሐፍ ኢይቤኑ ስድዳ ለአ
መት ምስለ ወልዳ እስመ ኢይወርስ ወልደ አመት
ምስለ ወልደ አግዓዚት ።
፴፩ ወንሕነሰ ይእዜ አኀዊነ ኢኮነ ውሉደ አመት ዘእን
በለ ዘአግዓዚት፣ እስመ ክርስቶስ አግዓዘነ ።

ምዕራፍ ፭፤

<u>ክፍል ፰፣ ዘከመ ኢይደሉ ተዓቅፎ በእንተ ግዝረት ።</u>

፩ ቁሙ እንከ ወኢትሑሩ ዳግመ ውስተ አርዑተ ቅኔ።

፪ ናሁ አነ ጳውሎስ እብለክሙ እምከመ ትትገዘሩ
በኀበ ክርስቶስ ኢይበቍዐክሙ ምንተኒ ።

፫ ወካዕበ አሰምዕ ለኵሉ ብእሲ ግዙር ከመ ይደልዎ
ይግበር ኵሎ ሕገ ኦሪት ።
፬ ተሰዐርክሙ እምክርስቶስ እለ በኦሪት ተኀሥሡ ትጽ
ደቁ ወወደቅሙ እምጸጋሁ ።
፭ ወንሕነሰ በመንፈስ ወበአሚን ንሴፎ ንጽደቅ ።

፮ እስመ በኀበ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ተገዝሮኒ
ኢይበቍዕ ወኢተገዝሮኒ ኢያሰልጥ ዘእንበለ ዳእሙ
በአሚን ወበተፋቅሮ ።

፯ ትካትሰ ሠናየ ሮጽክሙ ።
፰ መኑ አዕቀፈክሙ ከመ ኢትእመኑ በጽድቅ እስመዝ

ግን ከዕቁባቲቱ የተወለደው ልደቱ ልዩ ነው፤ በሰው ፳፫
ልማድ ተወልዷል፤ ከእመቤቲቱ የተወለደው ግን
እግዚአብሔር በሰጠው ተስፋ ተወልዷል ። ዘፍ፣ ፲፰
፲። ሮሜ ፱ ፯ - ፱ ።
የሁለቱ ሥርዓት ምሳሌ ይህ ነው፤ አንዲቱ ከደብረ ፳፬
ሲና ለተገዢነት ተወለደች፤ እሷም አጋር ናት ።
ምዕ፣ ፫ ፩ ። ሮሜ ፰ ፲፭ ።
ሲናም በዓረብ አገር ያለች ተራራ ናት፤ በታችኛው ፳፭
ዓለም ከምትኖረው ከምድራዊት ኢየሩሳሌም ትነፃፀ
ራለች ከልጆቿም ጋር ትገዛለች ።
የላይኛይቱ ኢየሩሳሌም ግን ከባርነት ነፃ ናት እሷም ፳፮
እናታችን ናት ። ዕብ፣ ፲፪ ፳፪ ።
የማትወልድ መካን ፈጽሞ ደስ ይላታል ምጥ የማ ፳፯
ታውቀውም ደስ ብሏት ዕልል ትላለች፤ ባል ካላት
ይልቅ የተፈታችቱ ልጆች ብዙዎች ናቸውና ።
ኢሳ፣ ፶፬ ፩ ።
ወንድሞቻችን! እኛስ እንደ ይስሐቅ የተስፋ ልጆች ፳፰
ነን ። ሮሜ ፱ ፯ ።
ነገር ግን በሥጋዊ ግብር የተወለደው በመንፈሳዊ ፳፱
ግብር የተወለደውን እንዳሳደደው ያሁል ዛሬም
እንዲሁ ነው ።
ግን መጽሐፍ ምን አለ የባርያይቱ ልጅ ከእመቤቲቱ ፴
ልጅ ጋር አይወርስምና ባርያይቱን ከነልጅዋ አስወ
ጥተህ ስደዳት አላለምን? ። ዘፍጥ፣ ፳፩ ፲ - ፲፪ ።
ወንድሞቻችን! አሁንም እኛስ የባርያ ልጆች አይ ፴፩
ደለንም የእመቤት ልጆች ነን እንጂ፤ ክርስቶስ ነፃ
አውጥቶናልና ። ምዕ ፫ ፳፱ ።

ም ዕ ራ ፍ ፭ ።

<u>ክፍል ፰፣ ስለ ግዝረት መጠራጠር እንደማይገባ ።</u>

እንግዲህ ፀኑ ወደ ባርነት ቀንበርም እንደገና አት ፩
መለሱ ። ምዕ፣ ፬ ፭ - ፴፩ ። ግብ፣ ሐዋ፣ ፲፭ ፲ ።
እነሆ እኔ ጳውሎስ እነግራችኋለሁ ከተገዘራችሁ ፪
በክርስቶስ ዘንድ ምንም ምን አይረባችሁም አይ
ጠቅማችሁም ።
ዳግመኛም ለተገዘረ ሰው ሁሉ የኦሪትን ሕግ መፈ ፫
ጸም እንደሚገባው አዳኛለሁ ።
በኦሪት ልትጸድቁ የምትሹ ከክርስቶስ ተለያችሁ ፬
ከጸጋውም ወደቃችሁ ። ምዕ ፪ ፳፩። ሮሜ ፯ ፪-፫ ።
እኛ ግን በመንፈስ በሃይማኖት ልንጸድቅ ተስፋ ፭
እናደርጋለን ። ፪ ጢሞ፣ ፬ ፰ ።
በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ዘንድ በሃይማኖትና ፮
በፍቅር መጽናት ነው እንጂ፤ መገዘርም አይጠቅ
ምምና አለመገዘርም ግዳጅ አይፈጽምምና። ምዕ ፮
፲፭። ፩ ቆሮ ፯ ፲፱ ።
ቀድሞማ መልካም ተፋጥናችሁ ነበር። ም ፫ ፩ ። ፯
በውነት እንዳታምኑ ማን አሰናከላችሁ? ይህ አካ ፰

ሩፀትክሙ ኢኮነ ኀበ ውእቱ ዘጸውዓክሙ ።
፱ እኩኑ ኅዳጥ ብኁዕ ብዙኀ ሐሪፀ ያብኅዕ ።

፲ አንሰ ተአመንኩክሙ በእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ
ከመ ኢተሐልዩ ባዕደ ወዘሰ የሃውከክሙ ይፀውር
ደይኖ መኑሂ ዘኮነ ክዊኖ ።
፲፩ ወአንሰ አኀውየ ለእመ ግዝረተ እሰብክ ለምንትኑ
እንከ እዴገን ተሰዕረኑ እንከ ትዕይርተ መስቀሉ
ለክርስቶስ ።
፲፪ ርቱዕ ይንትጉ እለ የሀውኩክሙ ።

<u>ክፍል ፱፡ ዘከመ ይደሉ ተፋቅሮ ምስለ ቢጽ ።</u>

፲፫ ወአንትሙሰ ለግዕዛን ተጸዋዕክሙ አኀውየ ወዳእሙ
ኢትግበሩ ላቲ ምክንያተ ለግዕዛንክሙ በፍትወተ
ሥጋክሙ፤ ወበተፋቅሮ ተቀንዩ ለቢጽክሙ ።

፲፬ እስመ አሐዱ ቃል ይፌጽሞ ለኵሉ ሕግ፡ አፍቅር
ቢጸከ ከመ ነፍስከ ።

፲፭ ወእመሰ በበይናቲክሙ ትትባልዑ ወትትናሰኩ ተኀ
ልቆ ትርፈክሙ ።
፲፮ እብለክሙ በመንፈስ ሑሩ ወፍትወተ ሥጋክሙ
ኢትግበሩ ።
፲፯ እስመ ሥጋኒ ይፈቱ ዘኢይፈቱ መንፈስ ወመንፈስኒ
ይፈቱ ዘኢይፈቱ ሥጋ፡ ወይትአበዩ በበይናቲሆሙ
ከመ ኢትግበሩ ዘትፈቅዱ ።
፲፰ ወእመሰ ዘመንፈስ ትትልዉ ወፃእክሙ እምኦሪት ።

፲፱ ወይትዐወቅ ምግባሩ ለሥጋ ዝሙት ርኵስ ወምርዓት።

፳ አጣዕዎ ሥራይ ጽልእ ትዝህርት ትውዝፍት ቅን
አት መዓት ኑፋቄ ተቃኅዎ ተሐምሞ ተቃትሎ
ስክረት ወዘአምሳሊሁ ለዝንቱ ።
፳፩ በከመ አቅደምኩ ነጊሮተክሙ ዘዘንተ ይገብር ኢይ
ሬኢ መንግሥተ እግዚአብሔር ።
፳፪ ወፍሬሁሰ ለመንፈስ ቅዱስ ተፋቅሮ ፍሥሐ ሰላም
ትዕግሥት ምጽዋት ኂሩት ሃይማኖት የውሃት ኢዘ
ምዎት ።
፳፫ አልቦ ዘይኄይስ እምዝ ሕግ ።
፳፬ ወእለሰ በኢየሱስ ክርስቶስ ሰቀሉ ሥጋሆሙ ምስለ
ፍትወት ወምስለ ኃጢአት ።
፳፭ ወይእዜሰ በመንፈስ ንሕየው ወዘመንፈስ ንግበር ።

፳፮ ወኢንኩን ዝኑራነ ወኢትትሐመዩ በበይናቲክሙ
ወኢትትኀሠሡ በበይናቲክሙ ።



ሄዳችሁ እሱ ወደ ጠራችሁ አይደለምና ። ም ፩ ፮።
ጥቂት ርሾ ብዙውን ዱቄት መፃፃ ያደርገው ፱
የለምን ? ።
በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ሌላ እንዳታስቡ እኔ ፲
ተማምኘችሁ ነበር ፤ የሚያውካችሁ ግን የሆነ ሆኖ
ማንም ቢሆን ፍዳውን ይቀበላል ። ፪ ቆሮ ፪ ፫ ።
ወንድሞቼ! እኔ ግዝረትን የምሰብክ ከሆነ ለምን ፲፩
እፈለጋለሁ የክርስቶስ የመስቀሉ መከራ ቀረን?
፩ ቆሮ ፩ ፳፫ ።
የሚያውኳችሁ ሰዎች ሊለዩ ይገባል። መዝ ፲፪ ፬ ። ፲፪

<u>ክፍል ፱፡ ከባልንጀራ ጋር ፍቅር እንዲገባ ።</u>

ወንድሞቼ! እናንተስ ለነፃነት ተጠርታችኋል ግን ፲፫
በሥጋችሁ ፈቃድ ብቻ ለነፃነታችሁ ምክንያት አታ
ድርጉባት ለወንድሞቻችሁም በፍቅር ታዘዙ ።
፩ ቆሮ ፰ ፱ ።
አንድ ቃል ሕግን ሁሉ ይፈጽመዋልና ይኸውም ፲፬
“ወንድምህን እንደ ራስህ ውደድ„ ማለት ነው። ዘሌ
፲፱ ፲፰። ማር፡ ፲፪ ፴፩ ።
እርስ በርሳችሁ የምትናከሱ የምትበሉ ከሆነ ግን፤ ፲፭
መተላለቅ ቀርቷችኋል ። ፪ ቆሮ ፲፪ ፳ ።
በመንፈሳዊ ግብር ፀንታችሁ ኑሩ፤ የሥጋችሁን ፲፮
ፈቃድ አትሥሩ እላችኋለሁ ። ሮሜ ፮ ፲፪ ።
ሥጋ ነፍስ የማትሻውን ይሻልና ነፍስም ሥጋ የማይ ፲፯
ሻውን ትሻለችና፤ የምትሹትን እንዳታደርጉ እርስ
በርሳቸው ይጣላሉ ። ሮሜ ፯ ፲፭ - ፳፫ ።
የነፍስን ፈቃድ የምትከተሉ ከሆናችሁ፤ ከኦሪት ፲፰
ተለይታችኋል ።
የሥጋ ምግባሩ ዝሙት ርኵሰት መዳራት እንደሆነ ፲፱
ይታወቃል ። ፩ ቆሮ ፮ ፱ ።
ጣዖት ማምለክ ሥራይ ማድረግ መጣላት ክርክር ፳
የምንዝር ጌጥ ቅናት ቍጣ፤ ጥርጥር፡ ፍክክር፡ ምቀ
ኝነት መጋደል፡ ስካር ይህንም የመሰለ ሁሉ ነው ።
አስቀድሜ እንደ ነገርኋችሁ ይህን የሚያደርግ የእግ ፳፩
ዚአብሔርን መንግሥት አያይም ። ሉቃ፡ ፳ ፴፬ ።
የመንፈስ ፍሬው ግን መፋቀር ደስታ ሰላም ትዕግ ፳፪
ሥት፡ ምጽዋት፡ ቸርነት፡ ሃይማኖት፡ ገርነት፡
ንጽሕና ነው ። ኤፌ፡ ፭ ፱ ። ያዕ፡ ፫ ፲፯ ።
ከዚህ የሚበልጥ ሕግ የለም ። ፩ ጢሞ ፩ ፱ ። ፳፫
በኢየሱስ ክርስቶስ ያመኑ ሰዎች ግን ሰውነታቸውን ፳፬
ከምኞትና ከኃጢአት ለዩ ። ሮሜ ፮ ፮። ቈላ ፫ ፭ ።
አሁንም በመንፈሳዊ ግብር ፀንተን እንኑር መንፈሳዊ ፳፭
ሥራም እንሥራ ። ሮሜ ፰ ፩ ።
ትዕቢተኞች አንሁን እርስ በርሳችሁ አትተማሙ ፳፮
እርስ በርሳችሁም አትካሰሱ ። ፊልጵ፡ ፪ ፫ ።

## ምዕራፍ ፮ ።

### ክፍል ፲ ፡ ዘከመ ይደሉ ተዓግሦ ላዕለ ቢጽ ።

፩ አኅዊነ ለእመቦ ብእሲ ዘስሕተ እምኔክሙ አንትሙ
እለ በመንፈስ ቅዱስ አጽንዕዎ በመንፈሰ የውሃት
እንዘ ትትዓቀቡ ለርእስክሙ ወኢትስሐቱ ።

፪ ወፁሩ ለቢጽክሙ ዘአክበዱ ላዕሌክሙ ወበቱ ትፌጽሙ ሕገ ክርስቶስ ።
፫ ወእልቦ ዘያስሕት ርእሶ ።
፬ ወኵሉ ያመክር ምግባሮ በዘይከውኖ ምክሐ ለርእሱ
ወእከ ለባዕድ ።
፭ እስመ ኵሉ ፆሮ ይፀውር ።
፮ ወይስምዖ ንዑሰ ክርስቲያን ለዝ ነገር ወይትመሀር
ኵሎ ሠናያተ ።
፯ ኢያስሕቱክሙ አልቦ ዘያስተዓብዶ ለእግዚአብሔር
ዘዘርአ ሰብእ የአርር ።
፰ ዘዘርአ ውስተ ሥጋሁ የአርር ሞተ ወዘዘርአ ውስተ
መንፈሱ የአርር ሕይወተ ዘለዓለም ።
፱ ወኢንትሃከይ ገቢረ ሠናይ እስመ በዕድሜሁ ነአርሮ ።

፲ እምጣነ ብነ ዕለት ንግበር ሠናየ ለኵሉ ወፈድፋደሰ
ለሰብአ ሃይማኖት ።
፲፩ ርእዩ ዘከመ ጸሐፍኩ ለክሙ በእደዊየ ።
፲፪ ወእለሰ ይፈቅዱ ያድልዉ ለገጽ እሙንቱ ያጌብሩ
ክሙ ትትገዘሩ ፡ ዳእሙ ከመ ኢትትልዉ መስቀሎ
ለክርስቶስ ።
፲፫ ወእለሂ ተገዝሩ ኢዐቀቡ አሪተ ፡ ዳእሙ ፡ ይፈቅዱ
ለክሙ ትትገዘሩ ከመ በነፍስትክሙ ትዘኀሩ ።
፲፬ ወአንሰ ሐሰ ሊተ ኢይዜኀር ዘእንበለ በመስቀሉ
ለኢየሱስ ክርስቶስ እግዚእነ ወበኀቤሁ ምውት ዓለም
ወአነሂ ምውት በኀበ ዓለም ።
፲፭ እስመ በኢየሱስ ክርስቶስ ተገዝሮሂ ኢይበቍዕ
ወኢተገዝሮሂ ኢያሰልጥ ዘእንበለ ሐዳስ ፍጥረት ።

፲፮ ወላዕለ ኵሎሙ እለ ይነብሩ በዝንቱ ሕግ ሰላም
ወሣህል ፡ ወዲበ እስራኤል ዘእግዚአብሔር ።

፲፯ እምይእዜሰ አልቦ ዘያንጥየኒ አንሰ ሕማሞ ለክርስቶስ
እፀውር በሥጋየ ።
፲፰ ጸጋሁ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ምስለ መንፈስ
ክሙ አኃውየ ።

ተፈጸመት መልእክት ኀበ ሰብአ ገላትያ ወተጽሕፈት
በሮሜ ወተፈነወት በእደ ቲቶ ወስብሐት ለእግዚአብሔር።
አሜን ።

## ምዕራፍ ፮ ።

### ክፍል ፲ ፡ ባልንጀራን መታገሥ እንደሚገባ ።

ወንድሞቻችን ! ከእናንተ ወገን የተሳሳተ ቢኖር ፩
በመንፈስ ቅዱስ የፀናችሁ እናንተ ቅንአት ባለው
ልቡና አፅኑት ለራሳችሁ እየተጠበቃችሁ አት
በድሉ ። ማቴ፡ ፲፰ ፲፭ ። ያዕ፡ ፭ ፲፱ ።
ባልንጀሮቻችሁ ያከበዱባችሁን ሸክም ቻሉ ፡ በዚ ፪
ህም የክርስቶስን ሕግ ትፈጽማላችሁ ። ሮሜ ፲፬ ፩።
ራሱን የሚያስት አይኑር ። ፫
ለሌላ ሳይሆን ራሱ የሚመካ እንዲሆን ሁሉም ሥራ ፬
ውን ይመርምር ። ፪ ቆሮ ፲፫ ፭ ።
ሁሉም ሸክሙን ይሸከማልና ። ፪ ቆሮ ፭ ፲ ። ፭
ይህንንም ነገር ንኡስ ክርስቲያን ይስማው መልካ ፮
ሙንም ነገር ሁሉ ይማር ። ፩ ቆሮ ፱ ፲፬ ።
አያስቷችሁ እግዚአብሔርን የሚያስንፈው አይኑር ፯
ሰው የዘራውን ያጭዳል ።
ለሥጋው የዘራ ሞትን ያጭዳል ለመንፈሱም የዘራ ፰
የዘለዓለም ሕይወትን ያጭዳል ። ሮሜ ፰ ፲፫ ።
በጎ ሥራ መሥራትን ቸል አንበል በጊዜው እናገኘ ፱
ዋለንና ። ፪ ተሰ፡ ፫ ፲፫ ።
ጊዜ ሳለን ለሁሉ መልካም ሥራ እንሥራ ይልቁንም ፲
ለሃይማኖት ሰዎች ። ፪ ጴጥ፡ ፩ ፯ ።
በእጄ እንደ ጻፍኩላችሁ እዩ ። ፲፩
ለሰው ፊት ሊያደሉ የሚወዱ እነዚያ ግን እንዳት ፲፪
ገዘሩ ያስገድዷችኋል ፡ የክርስቶስን መከራ እንዳት
ቀበሉ ነው ። ም ፭ ፲፩ ። ፊልጵ፡ ፫ ፲፰ ።
የተገዘሩትም ኦሪትን አልጠበቁም ፡ በግዘርነታችሁ ፲፫
እንድትታበዩ እንድትገዘሩ ያግባቧችኋል እንጂ ።
እኔ ግን በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ መከራ እንጂ ፲፬
በሌላ አልመካም ፡ በእኔ ዘንድ ዓለም የሞተ ነው ፡
እኔም በዓለም ዘንድ የሞትኩ ነኝ ። ፩ ቆሮ ፩ ፴፩ ፪ ፪።
በኢየሱስ ክርስቶስ አዲስ ሰውነት ማግኘት ነው ፲፭
እንጂ መገዘርም አይጠቅምም አለመገዘርም አይ
ጐዳምና ። ም ፭ ፮ ። ፩ ቆሮ ፯ ፲፱ ።
በዚህ ሕግ ፀንተው ለሚኖሩ ሰዎች ሰላም ይሁንላ ፲፮
ቸው ይቅርታም የእግዚአብሔር ወገኖች በሆኑ እስ
ራኤል (ክርስቲያን) ይሁን ። መዝ ፻፳፭ ፭ ።
እንግዲህ ወዲህ የሚነዘንዘኝ አይኑር ፡ እኔ የኢየ ፲፯
ሱስ ክርስቶስን መከራ በሥጋዬ እቀበላለሁ ።
ወንድሞቼ ሆይ ! የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ጸጋ ፲፰
ከእናንተ ጋር ይሁን ።

በሮም ተጽፋ በቲቶ እጅ ወደ ገላትያ ሰዎች የተላ
ከች መልእክት ተፈጸመች ለእግዚአብሔር ምስጋና
ይሁን ። አሜን ።

# ኀበ ሰብአ ኤፌሶን።

## ምዕራፍ ፩።

### ክፍል ፩፡ ሥጋዌሁ ለክርስቶስ።

፩ እምጳውሎስ ሐዋርያሁ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ
በፈቃደ እግዚአብሔር ለቅዱሳን እለ በኤፌሶን ወም
እመናን በኢየሱስ ክርስቶስ።

፪ ሰላም ለክሙ ወጸጋ እግዚአብሔር አቡነ ወእግዚእነ
ኢየሱስ ክርስቶስ።

፫ ይትባረክ እግዚአብሔር አቡሁ ለእግዚእነ ኢየሱስ
ክርስቶስ ዘባረከነ በኵሉ በረከተ መንፈስ ቅዱስ ዘበ
ሰማያት በክርስቶስ ኢየሱስ።

፬ በከመ ኀረየነ ሎቱ እምቅድመ ይትፈጠር ዓለም ከመ
ይረስየነ ቅዱሳነ ወንጹሓነ በቅድሜሁ ዘእንበለ ነውር።

፭ ወበተፋቅሮ ሠርዐነ ትርሲተ ወልዱ በእንተ ኢየሱስ
ክርስቶስ በከመ ሥምረተ ፈቃዱ።

፮ ለክብር ወለስብሐት በጸጋሁ ዘጸገወነ በወልዱ ፍቁሩ።

፯ ዘበእንቲአሁ ረከብነ መድኀኒተ ወተኀድገ ለነ ኃጢ
አትነ በደሙ በከመ ብዕለ ጸጋሁ።

፰ ዘአፈድፈደ ላዕሌነ በኵሉ ጥበብ ወምክር።

፱ ወአርአየነ ምክረ ፈቃዱ በከመ ሥምረቱ በዘሠር
ዐነ በእንቲአሁ።

፲ ወአቀመ እስከ አመ ይበጽሕ ዕድሜሁ ከመ ይትሐ
ደስ ኵሉ ዘበሰማይ ወዘበምድር።

፲፩ ወከፈለነ በዘሠርዐነ እግዚአብሔር ወረድአነ በከመ
ምክረ ፈቃዱ።

፲፪ ከመ የሀበነ ምክረ ወስብሐተ ለእለ ተወከልነ በክር
ስቶስ ኢየሱስ።

፲፫ ወአንትሙሂ ሰማዕክሙ ቃለ ጽድቀ ትምህርተ ሕይ
ወትክሙ ወአመንክሙ ወአተቡክሙ በመንፈስ
ቅዱስ ዘአሰፈወ።

፲፬ ዘውእቱ አረበነ ርስትነ ወመድኀኒተ ሕይወትነ በክ
ብረ ስብሐቲሁ።

### ክፍል ፪፡ በእንተ ተስፋ ጽዋዔ።

፲፭ ወበእንተዝ አነሂ ሰሚዕየ ሃይማኖተክሙ በእግዚእነ
ኢየሱስ ክርስቶስ ወዘከመ ታፈቅርዎሙ ለኵሎሙ
ቅዱሳን።

፲፮ ኢያንተጕ አአኵቶቶ በእንቲአክሙ ወተዘክሮተክሙ
በጸሎትየ።

፲፯ ከመ እግዚአብሔር አምላኩ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክር
ስቶስ አበ ስብሐት የሀብክሙ መንፈሰ ጥበብ ወይክ
ሥት ለክሙ ታእምሩ።

፲፰ ወያብርህ አዕይንተ አልባቢክሙ ወታእምሩ ምንት

# ወደ ኤፌሶን ሰዎች።

## ምዕራፍ ፩፤

### ክፍል ፩፡ ስለ ክርስቶስ ሰው መሆን።

በእግዚአብሔር ፈቃድ የጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ፩
ሐዋርያ ከሚሆን ከጳውሎስ የተላከች መልእክት
በኤፌሶን ላሉ ቅዱሳን በኢየሱስ ክርስቶስ ላመኑ
ምእመናን ትድረስ። ሮሜ ፩ ፯። ፩ ቆሮ፡ ፩ ፪።
ሰላም ለእናንተ ይሁን የአባታችን የእግዚአብሔር ፪
የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ጸጋ ይደርባችሁ።
በክርስቶስ ኢየሱስ ሰማያዊ ፍጹም በሆነው በመን ፫
ፈስ ቅዱስ በረከት ያከበረን የጌታችን የኢየሱስ ክርስ
ቶስ አባቱ እግዚአብሔር ይክበር ይመስገን። መዝ፡
፸፪ ፲፯። ምዕ፡ ፪ ፯።
በፊቱ ነውር የሌለብን ንጹሐን ቅዱሳን ያደርገን ፬
ዘንድ ዓለም ሳይፈጠር እንደመረጠን መጠን።
ዮሐ፡ ፲፭ ፲፮። ሮሜ ፰ ፳፱። ምዕ፡ ፭ ፳፯።
ስለ ኢየሱስ ክርስቶስም እንደ ውድ ፈቃዱ በፍ ፭
ቅር የልጁ ጌዋ አደረገን። ዮሐ፡ ፩ ፲፪።
በልጁ በወዳጁ በሰጠን በጸጋው ለክብር ለጌትነቱ ፮
እንበቃ ዘንድ። ኢሳ፡ ፵፫ ፳፩። ማር፡ ፫ ፲፯።
እንደ ቸርነቱ ብዛት በእሱ ምክንያት ደኅንነትን ፯
ያገኘን። ቈላ፡ ፩ ፲፬። ምዕ፡ ፪ ፯። ፫ ፰-፲፮።
ምክርን ጥበብን ሁሉ ያበዛልን። ፰
እሱን ለማገልገል በአዘጋጀን ገንዘብ እንደ ፈቃዱ ፱
ወዶ የፈጸመውን ምክሩን ገለጸልን። ሮሜ ፲፮ ፳፭።
በሰማይ በምድር ያለው ሁሉ እንዲታደስ ጊዜው ፲
የሚደርስበትን ወሰነ። ዕብ፡ ፱ ፲።
እግዚአብሔር በመደበልን መጠን ርስትን አገኘን ፲፩
ወዶ እንደ ሠራት ምክሩ ረዳን። ገላ፡ ፬ ፬።
በክርስቶስ ኢየሱስ ላመንነው ለእኛ ዕውቀትንና ፲፪
ክብርን ይሰጠን ዘንድ። ገላ፡ ፫ ፳፫-፳፭።
እናንተም መዳናችሁን የምትማሩበትን እውነተኛ ፲፫
ውን ቃል ሰምታችኋል አምናችሁም ተስፋ በደረገ
ላችሁ በመንፈስ ቅዱስ ከማያምኑት ለዩአችሁ።
ምዕ፡ ፬ ፴። ፪ ቆሮ፡ ፩ ፳፪።
ይኸውም የርስታችን ፈለማ በጌትነቱ ክብር ሕይወ ፲፬
ታችን የተገኘበት መድኀኒት ነው። ሮሜ ፰ ፳፫።

### ክፍል ፪፡ ስለ ሃይማኖት ጥሪ ተስፋ።

ስለዚህ እኔም በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ማመ ፲፭
ናችሁን ቅዱሳንንም ሁሉ መውደዳችሁን ሰምቼ።
ቈላ፡ ፩ ፬።
ስለ እናንተ እግዚአብሔርን ከማመስገን በጸሎቴም ፲፮
እናንተን ከማሰብ አልበዘንኩም።
የክብር ባለቤት የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ አባቱ ፲፯
እግዚአብሔር የጥበብን ሀብት እንዲሰጣችሁ ዕውቀ
ቱንም እንዲገልጽላችሁ። ሮሜ ፮ ፬።
የተጠራችሁበት ተስፋ ምን እንደሆነ ለቅዱሳን ርስት ፲፰

ኵሉ ለመድኩ ርኂበኒ ወጸጊበኒ ሐሚመኒ ወተፈ
ሥሖኒ ።
፲፫ ኵሎ እክል በዘውእቱ አክሀለኒ ክርስቶስ ።

፲፬ ወባሕቱ ሠናየ ገበርክሙ ዘተሣተፍክሙ በሕማምየ።

፲፭ ተአምሩ አንትሙ ሰብአ ፊልጵስዩስ በቀዳሚ ትም
ሀርት አመ መጻእኩ እመቄዶንያ ከመ ኢኀብሩ ምስ
ሌየ አሐዱኒ እምቤተ ክርስቲያን ኢ. በውሂብ ወኢ.
በነሢእ ዘእንበለ ዳእሙ በሕቲትክሙ ።

፲፮ ዓዲ በተሰሎንቄኒ ምእረ ወክልዐበ ፈኖክሙ ሊተ ለች
ካዝየ ።
፲፯ አኮ ሀብተክሙ ፈቂድየ ዘእዜክር ዘንተ ዳእሙ አን
ሥሥ ከመ ይሥመር በላዕሌክሙ ፍሬ ጽድቅ ።

፲፰ ወናሁ ተወከፍኩ ኵሎ ዘፈኖክሙ ኀቤየ የአክለኒ
ወዘተርፈ ሠለጥኩ በዘአብጽሐ ሊተ አፍሮዲጡ ዘእ
ምኀቤክሙ መዓዛ ሠናየ ወመሥዋዕተ ኅሩየ ወሥ
ሙረ በኀበ እግዚአብሔር ።
፲፱ ወአምላኪየ ይፈጽም ለክሙ ኵሎ መፍቅደክሙ
በከመ ብዕለ ስብሐቲሁ ለኢየሱስ ክርስቶስ ።
፳ ወእግዚአብሔር አቡነ ዘሎቱ ስብሐት ለዓለመ ዓለም
አሜን ።
፳፩ አምኁ ኵሎ ቅዱሳነ በኢየሱስ ክርስቶስ፡ አምኁ
ክሙ አኃዊነ እለ ኀቤየ ።

፳፪ ወይኤምኁክሙ ኵሎሙ ቅዱሳን፥ ወፈድፋደሰ እለ
እምሰብአ ቄሣር ቤተ ንጉሥ ።

፳፫ ጸጋሁ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ምስለ መንፈስ
ክሙ አሜን ።

~~

ተፈጸመት መልእክት ኀበ ሰብአ ፊልጵስዩስ ወተጽ
ሕፈት በሮሜ ወተፈነወት ምስለ ጢሞቴዎስ ወአፍሮዲጡ።
ወስብሐት ለእግዚአብሔር ፥ አሜን ።



ለምጂዋለሁ ራቡንም ጥጋቡንም መከራውንም መደ
ሰቱንም ። ፪ ቆሮ፥ ፯ ፲ ። ፲፩ - ፳፯ ።
እሱ ክርስቶስ በሰቻለኝ መጠን ሁሉን እችላለሁ ። ፲፫
ኢሳ፥ ፵ ፳፱ - ፴፩ ። ፪ ቆሮ፥ ፲፪ ፲ ።
ነገር ግን በመከራዬ ጊዜ ተባባሪዎች የሆናችሁ ፲፬
መልካም አደረጋችሁ ።
እናንተ የፊልጵስዩስ ሰዎች ! በመጀመሪያው ትምህ ፲፭
ርት ከመቄዶንያ ወደ እናንተ በመጣሁ ጊዜ በመስ
ጠትም በመንሳትም ከእናንተ ብቻ በቀር ከምእመናን
አንድ እንኳ ከእኔ ጋር እንዳልተባበረ ታውቃላችሁ ።
፪ ቆሮ፥ ፲፩ ፱ ። ፩ ጢሞ፥ ፩ ፫ ።
በተሰሎንቄም ሳለሁ አንድ ጊዜ ሁለት ጊዜ ለችግሬ ፲፮
ላካችሁልኝ ። ግብ፥ ሐዋ፥ ፲፯ ፩ ።
ይህን የምናገር ስጦታችሁን ፈልጌ አይደለም በእና ፲፯
ንተ ላይ የጽድቅ ፍሬ ይበዛ ዘንድ ወድጄ ነው
እንጂ ። ፩ ቆሮ፥ ፱ ፲፩ ። ቲቶ፥ ፫ ፲፬ ።
እነሆ የላካችሁልኝ ሁሉ ተቀብያለሁ በቅቶኛል በቀ ፲፰
ረውም ከእናንተ ወገን የሚሆን አፍሮዲጡ በመጣ
ልኝ በእግዚአብሔር ዘንድ ያማረ የተወደደ መሥዋ
ዕትና በጎ መዓዛ አሟላሁ ። ኤፌ፥ ፭ ፪ ። ዕብ፥ ፲፫ ፲፯ ።
ፈጣሪዬ እንደ ጌትነቱ ምላት ስፋት በኢየሱስ ክር ፲፱
ስቶስ የምትሹትን ሁሉ ይፈጽምላችሁ ። ፪ ቆሮ ፱ ፰ ።
እግዚአብሔር አበታችን ይፈጽምላችሁ ለዘለዓለም ፳
ክብር ምስጋና የሚገባው በእውነት ። ገላ ፩ ፬ - ፭ ።
በኢየሱስ ክርስቶስ ምእመናንን ሁሉ ቸር አላችሁን ፳፩
በሉ ከእኔ ዘንድ ያሉ ወንድሞቻችን ሰላምታ ያቀር
ቡላችኋል ። ፩ ቆሮ፥ ፲፮ ፳ ።
ቅዱሳን ሁሉ ሰላምታ ያቀርቡላችኋል ፥ ይልቁንም ፳፪
ከቄሣር ትውልድ ያላቸው ንጉሣውያን ቤተ ሰብ
ቸር አላችሁ ይሏችኋል ። ፪ ቆሮ፥ ፲፫ ፲፪ ።
የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ጸጋ ከእናንተ ጋር ፳፫
ይሁን ፥ አሜን በእውነት ። ፩ ቆሮ፥ ፲፮ ፲፫ ።

~~

በሮም ተጽፋ በጢሞቴዎስና በአፍሮዲጡ እጅ ወደ ፊል
ጵስዩስ የተላከች መልእክት ተፈጸመች ።
ለእግዚአብሔር ክብር ምስጋና ይሁን ፥ አሜን ።



# ኀበ ሰብአ ተሰሎንቄ ፩ ። || ወደ ተሰሎንቄ ሰዎች ፩ ።

## ምዕራፍ ፩፤

### ክፍል ፩፡ ዘከመ ይደሉ ከዊነ አርአያ ለአኀው ።

፩ እምጳውሎስ ወስልዋኖስ ወጢሞቴዎስ ለቤተ ክርስ
ቲያን ዘተሰሎንቄ ምእመናን በእግዚአብሔር አቡነ
ወእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ሰላም ለከሙ ወጸጋ
እግዚአብሔር አቡነ ወእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ።
፪ ነአኵቶ ለእግዚአብሔር ዘልፈ በእንቲአክሙ ወንዜ
ክረክሙ ወትረ በጸሎትነ ።
፫ ወንዜክር በቅድመ እግዚአብሔር አቡነ ግብረ ሃይ
ማኖትክሙ ወፅንዐ ፍቅርክሙ ወትዕግሥተ ተስፋ
ክሙ በእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ።
፬ ወነአምር አኃዊነ ፍቁራነ ዘከመ ኀረየክሙ እግዚ
አብሔር ።
፭ እስመ ኢኮነ ትምህርትነ ኀቤክሙ በነገር ባሕቲቱ
ዓዲ በኃይልኒ ወበመንፈስ ቅዱስ ወበስኢል ምእ
መን፡ ወአንትሙሂ ተአምሩ ዘከመ ኮነ በኀቤክሙ
በእንቲአክሙ ።
፮ ወናሁ ኪያነ ተመሰልክሙ ወተወከፍክሙ ቃለ እግ
ዚአብሔር በብዙኅ ሕማም ምስለ ፍሥሐ በመን
ፈስ ቅዱስ ።
፯ ወኮንክምዎሙ አርአያ ለእለ አምኑ ኵሎሙ እለ
በመቄዶንያ ወአካይያ ።
፰ እስመ እምኀቤክሙ ተምሀሩ ቃለ እግዚአብሔር
ወሰምዑ ወአኮ በመቄዶንያ ወአካይያ ባሕቲቱ ዓዲ
በኵሉ በሐውርት ተሰምዐት ሃይማኖትክሙ በእግ
ዚአብሔር ወኢንፈቅድ ንሕነ ምንተኒ ንንግር በእን
ቲአክሙ ።
፱ ለሊሆሙ የአምሩ ዘከመ በእነ ኀቤክሙ ወዘከመ
ተመየጥክሙ ኀበ እግዚአብሔር እምአምልከ ጣዖት
ከመ ትትቀነዩ ለአምላክ ሕያው ወጻድቅ ።
፲ እንዘ ትሴፈውዎ ለወልዱ እምሰማያት ዘተንሥአ
እሙታን ኢየሱስ ክርስቶስ ወውእቱ ያድኅነነ እመ
ንሱት ዘይመጽእ ።

## ምዕራፍ ፩ ።

### ክፍል ፩፡ ለወንድሞች አብነት መሆን ስለሚገባ።

ከጳውሎስ ከስልዋኖስና ከጢሞቴዎስ በተሰሎንቄ ፩
ላሉ በአባታችን በእግዚአብሔር በጌታችን በኢየ
ሱስ ክርስቶስ ላመኑ ምእመናን ትድረስ ሰላም ለእና
ንተ ይሁን የአባታችን የእግዚአብሔር የጌታችን
የኢየሱስ ክርስቶስ ጸጋ ይደርባችሁ ። ግ ሐ ፲፮ ፲፱ ።
ስለ እናንተ እግዚአብሔርን ዘወትር እናመሰግነዋለን ፪
ሁል ጊዜም በጸሎታችን እናስባችኋለን ።
በአባታችን በእግዚአብሔር ፊት የሃይማኖታችሁን ፫
ሥራ፡ የፍቅራችሁን ፅናት በጌታችን በኢየሱስ ክር
ስቶስ የሚሆን የአለኝታችሁን ትዕግሥት እናስባለን።
ዮሐ ፮ ፳፱ ። ፩ ቆሮ ፲፫ ፲፫ ።
የተወደዳችሁ ወንድሞቻችን! እግዚአብሔር እንደ ፬
መረጣችሁ እናውቃለን ። ቈላ ፫ ፲፪ ።
ለእናንተ ያስተማርነው ትምህርታችን በነገር ብቻ ፭
አይደለምና ተአምራትን በማድረግ በተቀደሰ ፈ
ቃድ በታመነ ጸሎትም ነው እንጂ፡ እናንተም ስለ
እናንት በእናንተ ዘንድ የሆነውን ታውቃላችሁ ።
፩ ቆሮ ፪ ፭ ።
እነሆ እኛን መስላችኋልና ለመንፈስ ቅዱስ እያላ ፮
ችሁ በብዙ መከራ የእግዚአብሔርን ቃል ተቀብላ
ችኋልና ። ፩ ቆሮ ፬ ፲፮ ።
በመቄዶንያና በአካይያ ላመኑም ሁሉ ምሳሌ ሁናች ፯
ኋቸዋል ። ምዕ ፬ ፲ ።
የጌታችን ቃል ከእናንተ ዘንድ ተምረው አምነዋ ፰
ልና በመቄዶንያና በአካይያ ብቻ አይደለም በእግዚአ
ብሔር ማመናችሁ በያገሩ ተሰምታለች እንጂ፡ እኛ
ስለ እናንተ ምንም ምን ልንናገር አንሻም ።
ሮሜ ፩ ፰ ።
እኛ ለማስተማር ወደ እናንተ እንደመጣን ሕያውና ፱
እውነተኛ ለሆነ አምላክ አገልጋዮች ልትሆኑ ከጣ
ዖት አምልኮ ወደ እግዚአብሔር እንደ ተመለሳችሁ
እነሱ ያውቃሉና ። ፩ ቆሮ ፲፪ ፪ ።
ከሰማይ የወረደውን ልጁን ተስፋ አድርጋችሁ ፲
እሱም ከሙታን ተለይቶ የተነሣ ኢየሱስ ክርስቶስ
ነው፡ እሱ ከሚመጣው መከራ ያድነናል ብላችሁ ።
ግብ፡ ሐዋ፡ ፩ ፲፩ ። ፊልጵ ፫ ፳ ።

ምዕራፍ ፪ ፡

**ክፍል ፪ ፡ በእንተ ምሂር በተየውሆ ።**

፩ ለሊክሙ ተአምሩ አኀዊነ ዘከመ ገበርነ ለክሙ ወኢ
ከነ በከንቱ በዊአትነ ኀቤክሙ ።
፪ ዳእሙ ሐመምነ ወተጽእልነ ዘከመ ተአምሩ በፊል
ጵስዩስ ወአሚሃ ነገርናክሙ በብዙኀ ፃማ ትምህርተ
ክርስቶስ በሞገሱ ለአምላክነ ።

፫ እስመ ኢኮነ ትምህርትነ ዘስሒት ወዘርኩስ ወኢኮነ
ዘጽልሑት ።
፬ ዳእሙ በዘአመከረነ እግዚአብሔር ወተአመነነ በት
ምህርተ ወንጌሉ ከማሁ ንነግር ወአኮ ከመ ዘለሰብአ
ያደሉ ዘእንበለ ለእግዚአብሔር ዘአመከረነ ልበነ ።

፭ ወእምአመ ኮነ ኢየዋህናክሙ በቃል በከመ ተአ
ምሩ ወኢተዐገልናክሙ በምክንያት ፡ ስምዕነ እግዚ
አብሔር በዝንቱ ።
፮ ወኢንፈቅድ ያድሉ ለነ ሰብእ ኢ. አንትሙ ወኢ በ
ዕድ እንዘ ንክል አክብዶ ከመ ሐዋርያተ ክርስቶስ ።

፯ ዳእሙ ኮነ ከመ ሕፃናት በማእከሌክሙ ።
፰ ወከመ ሐፃኒት እንተ ተሐዝል ደቂቃ ፡ ከማሁ ንሕነኒ
ናፈቅረክሙ ወንጽሕቅ ለክሙ ከመ ንመጡክሙ
ወአኮ ባሕቲቶ ወንጌለ እግዚአብሔር ፡ ዓዲ ነፍስነሂ
እስመ ፍቁራነ ኮንክሙነ ።

፱ ወተዘከሩ አኀዊነ ፃማነ ወሥራሐነ መዓልተ ወሌ
ሊተ ኮነ ንትጌበር ከመ ኢናክብድ ላዕለ አሐዱሂ
እምውስቴትክሙ ።
፲ ወለሊክሙ ሰማዕትነ ወእግዚአብሔር ዘከመ ሰበክነ
ለክሙ ትምህርተ ወንጌሉ ለእግዚአብሔር በጽድቅ
ወበርትዕ ወበንጽሕ በኀበ ኵሉሙ እለ የአምኑ ።

፲፩ ዘከመ ተአምሩ ለለአሐዱ አሐዱ እምውስቴትክሙ
ከመ አብ ለወልዱ ናስተበቍዐክሙ ወንናዝዘክሙ ።

፲፪ ወናሰምዕ ለክሙ ከመ ትሑሩ ወትሩፀ በዘይደልወ
ክሙ በኀበ እግዚአብሔር ዘጸውዐክሙ ውስተ መን
ግሥተ ስብሐቲሁ ።

**ክፍል ፫ ፡ በእንተ ተወክፎተ ቃል ዘእግዚአብሔር ።**

፲፫ በእንተዝ ንሕነሂ ዘልፈ ነአኵቶ ለእግዚአብሔር
እስመ ተወክፍክሙ ቃለ ትእዛዙ ለእግዚአብሔር
ወአኮ ቃለ ዜና ሰብእ አላ አማን ከማሁ ቃለ እግዚ
አብሔር ወይረድአክሙሂ ለገቢር ለእለ ተአመንክሙ ፤

ምዕራፍ ፪ ።

**ክፍል ፪ ፡ በየዋህነት ሆኖ ስለ ማስተማር ።**

ወንድሞቻችን! ለናንተ ያደረግነውን ታውቃላችሁ ፡ ፩
እናንተን ማስተማራችን በከንቱ አይደለምና ።
እንደምታውቁት በፊልጵስዩስ መከራን ተቀበልን ፪
ተሰደብን እንጂ ፡ በፈጣሪያችን አጋዥነት ያን ጊዜም
የክርስቶስን ወንጌል እንዳስተማርናችሁ ታውቃ
ላችሁ ። ግብ ሐዋ ፲፮ ፳፪ ።
ትምህርታችን የማሳሳት የማራከስ አይደለምና የሽን ፫
ገላም አይደለምና ።
እግዚአብሔር በመረመረን ወንጌሉን ለማስተማር ፬
ትበቃላችሁ ባለን ገንዘብ እንዲሁ እናስተምራለን
እንጂ ፡ ልቡናችንን ለመረመረው ለእግዚአብሔር
እንጂ ለሰው ይምሰል እንደሚሠራ አይደለምና ።
ከሆነም ጀምሮ እንደምታውቁት በቃል አላለዘብና ፭
ችሁም በምክንያትም ገንዘባችሁን አልበላንም ፡
በዚህ እግዚአብሔር ምስክራችን ነው ።
የክርስቶስ ሐዋርያት እንደ መሆናችን መጠን ማዘዝ ፮
ሲቻለን እናንተም ሆነ ሌላ ሰው ሊያደላልን
አንሻም ። ዮሐ ፭ ፵፩ - ፵፬ ። ግብ ሐዋ ፳ ፴፫ ።
በመካከላችሁ እንደ ሕፃናት ሆነ እንጂ ። ፯
ልጆቿን እንደምታሳድግ እንደ ሞግዚት እኛም ፰
እንዲሁ እንወዳችኋለን ፡ ልንሰጣችሁም እናስበችኋ
ለን ፡ ግን የእግዚአብሔርን ወንጌል ብቻ አይደለም ፡
ሰውነታችንንም ጭምር ነው እንጂ ወዳጆቻችን ናች
ሁና ። ሮሜ ፩ ፲፩ ።
ወንድሞቻችን! ድካማችንን ጥረታችንን አስቡ ከእ ፱
ናንተ ወገን አንዱን ስንኳ እንዳናስቸግር ቀንም
ሌሊትም እንሠራ ነበር ። ፪ ቆሮ ፲፩ ፱ ።
በሚያምኑት ሁሉ ዘንድ የእግዚአብሔር ወንጌልን ፲
በእውነት በቀጥተኛነት በንጽሕና እንደ ሰበክንላ
ችሁ እናንተ ምስክሮቻችን ናችሁ እግዚአብሔርም
ምስክራችን ነው ። ፩ ጢሞ ፫ ፪ ።
ከእናንተ እያንዳንዳችሁ እንደምታውቁት አባት ፲፩
ለልጁ እንደሚያስብ እናበብላችኋለን እናፅናናች
ኋለን ።
ወደ ጌትነቱ መንግሥት ወደ ጠራችሁ ወደ እግዚ ፲፪
አብሔር በሚገባችሁ ተፋጥናችሁ ትሄዱ ዘንድ እና
ዳኝባችኋለን ። ኤፌ ፬ ፩ ።

**ክፍል ፫፡ የእግዚአብሔርን ቃል ስለ መቀበል።**

ስለዚህ እኛም ዘወትር እግዚአብሔርን እናመሰግነዋ ፲፫
ለን ፡ ሰው ያወራውን ቃል ያይደለ እግዚአብሔር
ያዘዘውን ቃል ተቀብላችኋልና ፡ በእውነት የእግዚአ
ብሔርን ቃል ነው እንጂ ያመናችሁት እናንተም
በሥራ ይረዳችኋል ። ምዕ ፩ ፭ ። ገላ ፩ ፲፩ ።

፲፬ ወአንትሙ አኀዊነ ተመሰልክሙ በቤተ ክርስቲያኑ
ለእግዚአብሔር እለ በይሁዳ ምእመናን በኢየሱስ
ክርስቶስ እስመ ሐመምክሙ አንትሙኒ እምሕዝብ
ክሙ በከመ ሐሙ እሙንቱሂ እምአይሁድ እለ ቀተ
ልዎ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ።
፲፭ ወለነቢያትኒ እለ እምውስቴቶሙ ሰደድዎሙ ወኪ
ያነሂ ወኢያሠምርዎ ለእግዚአብሔር ወይትቃረኑ
ምስለ ኵሉ ሰብእ ።
፲፮ ወይከልኡነ ኢንንግር ለአሕዛብ በዘየሐይዉ ከመ
ይትፈጸሞሙ ኃጢአቶሙ ለዝሉፉ ወናሁ በጽሖሙ
መቅሠፍቶሙ ዘለዓለም ።
፲፯ ወንሕነሰ አኀዊነ ከመ እጓለ ማውታ ኮነ እምኔክሙ
በዝመዋዕል ለገጽ ዳእሙ ወአኮሰ እምልብ ወፈድ
ፋደ ጽሕቅነ ንርአይ ገጸክሙ ።

፲፰ ወብዙኀ ፈቀድኩ እምጻእ ኀቤክሙ ለልየ ጳውሎስ
ምዕረ ወክዕበ ወአዕቀፈኒ ሰይጣን ።

፲፱ መኑ ተስፋነ ወፍሥሐነ ወአክሊለ ምክሕነ አኮኑ
አንትሙ በቅድመ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ በም
ጽአቱ ።
፳ እስመ አንትሙ ክብርነ ወፍሥሐነ ።

ምዕራፍ ፫ ፤

<u>ክፍል ፩ ፣ ዘከመ ኢይደሉ ቀቢጸ ተስፋ ።</u>

፩ ወስኢነነ ተዐግሦ አብደርነ ንንበር አቴና እሐተኔ
በሕቲትነ ።
፪ ወፈነውናሁ ለጢሞቴዎስ እኁነ ላእከ እግዚአብሔር
ወረድኤትነ በትምህርተ ክርስቶስ ከመ ያፅንዕክሙ
ወያስተብቍዕክሙ በእንተ ሃይማኖትክሙ ።

፫ ከመ ኢታንቀልቅሉ ወኢይቅብጽ አሐዱሂ እምውስ
ቴትክሙ በዛቲ ሕማምክሙ ፣ ተአምሩ ለሊክሙ ከመ
ዝንቱ ዳእሙ ይጸንሐነ ።
፬ ወእመ ሀሎኩ ኀቤክሙ ዘንተ ከመ አቀደምኩ ወነ
ገርኩክሙ ከመ ሀለወነ ንሕምም ወይሣቅዩነ፣ ወበ
ከመ አመርናክሙ ኮነ ውእቱ ።

፭ ወበእንተዝ አነሂ ስኢንየ ተዐግሦ ፈነውኩ ጢሞቴ
ዎስሃ ከመ አእምር ሃይማኖተክሙ እመበ ከመ አመ
ከረክሙ ዘያሜክር ወለከንቱ ይከውን ፃማነ ዘበእን
ቲአክሙ ።
፮ ወይእዜሰ እምአመ በጽሐ ጢሞቴዎስ ኀቤነ እምኀ
ቤክሙ ወዜነወነ ሃይማኖተክሙ ወተፋቅሮተክሙ
ወከመሂ ትዜከሩነ በሠናይ ዘልፈ ወትፈትዉ ትርአ
ዩነ በከመ ንፈቱ ንሕነሂ ርእዮተክሙ ።



ወንድሞቻችን! እናንተም በኢየሱስ ክርስቶስ ያሙኑ ፲፬
በይሁዳ ባሉ በእግዚአብሔር ማኅበር ተመሰላችሁ፣
እነሱ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስን ከገደሉት ከአይ
ሁድ መከራ እንደ ተቀበሉ እናንተም ከወገኖቻችሁ
መከራ ተቀብላችኋልና ።
ከእነሱ ወገን የነበሩት ነቢያትንም ያሳደዷቸው ፲፭
ነበር እኛንም ያሳድዱናል ፣ እግዚአብሔርን ደስ አያ
ሰኙትም ከሰው ሁሉ ጋር ይጣላሉ ። ግብ ሐዋ ፪ ፳፪ ።
እንዳይድኑ ለአሕዛብ እንዳንነግራቸው ይከለክሉናል ፣ ፲፮
ኃጢአታቸው ለዘለዓለሙ ይፈጸምባቸው ዘንድ
እነሆ የዘለዓለም የሚሆን መቅሠፍት ደረሰባቸው ።
ወንድሞቻችን! እኛስ በዚህ ወራት ከእናንተ የተነሣ ፲፯
እንደ ድኻ አደግ ሆነ፣ ነገር ግን ከፊታችን ነው እንጂ
ከልባችን ተለይታችሁ አይደለም ይልቁንም ፊታች
ሁን ልናይ ወደናል ። ሮሜ ፩ ፲፩ ።
እኔ ጳውሎስ ብዙ ጊዜ ወደ እናንተ ልመጣ ወደ ፲፰
ድኩ አንድ ጊዜ ሁለት ጊዜ ሞከርኩ ፣ ግን ሰይጣን
አሰናከለኝ ።
አለኝታችን ደስታችን የመመኪያችን ክብር ማነው? ፲፱
በመጣ ጊዜ በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ፊት
መመኪያችን እናንተ አይደላችሁምን ። ፊል ፪ ፲፮ ።
ክብራችን ደስታችን እናንተ ናችሁና ። ፳

ምዕራፍ ፫ ።

<u>ክፍል ፩ ፣ ተስፋ መቍረጥ ስለማይገባ ።</u>

መታገሥ ተስኖን ብቻችንን አንድ ወገን ሆነን በአ ፩
ቴና ልንኖር ወደድን ። ግብ፣ ሐዋ፣ ፲፯ ፲፬ - ፲፭ ።
የክርስቶስን ወንጌል በማስተማር አጋዢአችን የእግ ፪
ዚአብሔር አገልጋይ የሚሆን ወንድማችን ጢሞቴ
ዎስን ሰደድነው፣ በሃይማኖት እንዲያፀናችሁ ስለ
ሃይማኖታችሁ ይመክራችሁ ያስተምራችሁ ዘንድ ።
በዚች በመከራችሁ ከናንተ ወገን አንድ ስንኳ ፫
ተስፋ እንዳይቈርጥና እንዳትነዋወጡ ይህ ብቻ እን
ዲቈየን እናንተ ታውቃላችሁ ።
ከናንተ ዘንድ በነበርሁ ጊዜም መከራ እንቀበል ፬
ዘንድ እንዳለንና ሥቃይንም ያፀኑብን ዘንድ እንዳ
ለን ይህን አስቀድሜ ነግሬአችሁ ነበር እንደ ነገርና
ችሁም ያው ሆነ ።
እኔም መከራውን መታገሥ ተስኖኝ ሃይማኖታችሁን ፭
አውቅ ዘንድ የሚፈታተን ተፈታትኖአችሁ እንደ
ሆነ ብዬ ጢሞቴዎስን ሰደድሁ፣ ስለ እናንተ የደከ
ምነው ድካም ለከንቱ ይሆናል ብዬ ።
ዛሬ ግን ጢሞቴዎስ ከናንተ ዘንድ ደርሶ ወደኛ ከመ ፮
ጣና ሃይማኖታችሁንና ፍቅራችሁን ከነገረን ጀምሮ
ሁለ ጊዜም በበጎ ነገር እንደምታስቡንና ፣ እኛ እና
ንተን ልናያችሁ እንድንወድ ፣ እናንተም እኛን ልታ
ዩን እንድትወዱ ከነገረን ጀምሮ ።

# የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ሃይማኖትና ሥርዓት
The Ethiopian Orthodox Tewahido Church Faith and Order




፯ በእንተዝ ተፈሣሕነ አኀዊነ በእንተ ኵሉ ሕማምነ ወምንዳቤነ ዘበእንተ ሃይማኖትክሙ ።
፰ እስመ ይእዜ ነሐዩ ወእምከመ አንትሙ ቆምክሙ በእግዚእነ ።
፱ አየ አኰቴተ ንክል ዐሥዮቶ ለእግዚአብሔር ሀየ ንተ ኵሉ ፍሥሐነ ዘተፈሣሕነ በእንቲአክሙ ዘእን በለ ከመ ንጸሊ ኀበ አምላክነ መዓልተ ወሌሊተ ።
፲ ወፈድፋደሰ ንጼሊ ከመ ንርአይ ገጸክሙ ወይትፈጸም ሕፀፀ ሃይማኖትክሙ ።
፲፩ ወእግዚአብሔር አቡነ ወእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ያርትዕ ፍኖተነ ኀቤክሙ ።
፲፪ ወለክሙሂ ያብዝኃ ወይፈድፍድ ተፋቅሮተክሙ በበ ይናቲክሙ ወምስለ ኵሉ ለለአሐዱ አሐዱ በከመ ንሕነ ናፈቅረክሙ ለክሙ ።
፲፫ ወይጽናዕ ልብክሙ በንጽሕ ወበቅድሳት ለቅድመ እግዚአብሔር አቡነ አመ ምጽአተ እግዚእነ ኢየ ሱስ ክርስቶስ ምስለ ኵሎሙ ቅዱሳን ።

## ምዕራፍ ፬ ፤

### ክፍል ፰ ፡ በእንተ ርኂቅ እምዘዘኢአሁ ፈቃደ ሥጋ ።

፩ ወይእዜኒ አኀዊነ ንነግረክሙ ወናስተበቍዐክሙ በእ ግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ከመ ተአዘዝክሙ በኀቤነ በዘይደሉ ከመ ትሑሩ ወታሥምርዎ ለእግዚአብ ሔር በከመ ሖርክሙ ዓዲ ከመ ታብዝኁ ወታፈ ድፍዱ በዝንቱ ።
፪ ወተአምሩ ዘከመ አዘዝናክሙ በእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ።
፫ እሳመ ዝ ውእቱ ትእዛዙ ለእግዚአብሔር ወፈቃዱ ተቀድሶትክሙ ውእቱ ወከመ ትትዓቀቡ ወትርኀቁ እምዝሙት ።
፬ ወያእምር ኵሉ ለለአሐዱ ንዋዮ ወያጥርዮ በቅድሳት ወክብር ።
፭ ወኢትትመንሰዉ በፍትወት ከመ አረሚ እለ ኢየአ ምርዎ ለእግዚአብሔር ።
፮ ወኢትትሀበሉ ትግበሩ ዘንተ ወኢትትዐገሉ ቢጸ ክሙ ለኵሉ እስመ መስተበቅል እግዚአብሔር በእ ንተ ዝንቱ ኵሉ በከመ አቀደምኩ ነጊሮተክሙ ወአ ስማዕኩ ለክሙ ።
፯ እስመ ኢጸውዐነ እግዚአብሔር ለርኵስ ዘእንበለ ለቅድሳት ።
፰ ወይእዜኒ ዘክሕደሽ ለያእምር ከመ አኮ ለሰብእ ዘይ ክሕድ ዘእንበለ ለእግዚአብሔር፡ ዘወሀበክሙ መን ፈሰ ቅዱሰ ።
፱ ወበእንተሰ አፍቅሮ ቢጽክሙ ኢትፈቅዱ ንጽሐፍ ለክሙ ለሊክሙ ምሁራን በኀበ እግዚአብሔር ከመ ትትፋቀሩ በበይናቲክሙ ።



ወንድሞቻችን ! ስለዚህ ስለ ሃይማኖታችሁ በሚሆን ፯
በመከራችን በፀዋትወ መከራችን ደስ ይለናል ።
ዛሬ እናንተ በጌታችን አምናችሁ ከፀናችሁ ደስ ፰
ይለናልና ።
ስለ እናንተ ደስ ስላለን ለእግዚአብሔር ምን ያህል ፱
ምስጋና ልናቀርብለት እንችላለን ? በቀንም በሌሊ
ትም ወደ ፈጣሪያችን ከመጸለይ በቀር ።
ይልቁንም የሃይማኖታችሁ ሕፀፅ እንዲፈጸም ፊታ ፲
ችሁን እናይ ዘንድ እንጸልያለን ።
እግዚአብሔር አባታችን ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ፲፩
ወደ እናንተ ለመምጣት መንገዳችንን ያቅናልን ።
ለእናንተም እኛ እናንተን እንደምንወዳችሁ ከእና ፲፪
ንተ እያንዳንዱ እርስ በርሳችሁ ከሁሉም ከያንዳንዱ
ጋር መፋቀርን ፈጽሞ ያብዛላችሁ ።
ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከቅዱሳን ሁሉ ጋር በሚ ፲፫
መጣበት ጊዜ በአባታችን በእግዚአብሔር ፊት ለመ
ቆም ልባችሁ በንጽሕና በቅድስና ይፅና ። ዘካ፡ ፲፬ ፭፤
ራእ ዮሐ፡ ፳ ፲፩ ።

## ምዕራፍ ፬ ።

### ክፍል ፰ ፤ ከልዩ ልዩ ፈቃደ ሥጋ ስለ መራቅ ።

አሁንም ወንድሞቻችን ከእኛ ዘንድ እንደታዘዛችሁ ፩
በሚገባ ትኖሩ ዘንድ እግዚአብሔርንም ደስ ታሰኙት
ዘንድ እንነግራችኋለን ፤ ከዚህ በፊት እንደኖራችሁ
እንግዲህ ወዲህም አብዝታችሁ ትሠሩ ዘንድ እንማ
ልዳችኋለን ። ፪ ተሰ፡ ፫ ፲፪ ። ኤፌ፡ ፬ ፩ ።
በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ እንደ አዘዝናችሁ ፪
ታውቃላችሁ ።
የእግዚአብሔር ትእዛዙ ይህ ነውና ፈቃዱም ንጽ ፫
ሕና መያዛችሁ ነውና ፤ ከኃጢአት መራቃችሁ ነው
ከዝሙትም እንድትጠበቁና እንድትርቁ ነውና ።
ሁሉም እያንዳንዱ ገንዘቡን ይወቅ በንጽሕና በክ ፬
ብር ይጠብቀው ። ሮሜ ፮ ፲፱ ። ፩ ቆሮ ፮ ፲፫ - ፲፭ ።
እግዚአብሔርን እንደማያውቁት እንደ አረሚ በዝ ፭
ሙት ድል አትነሡ ። ቈላ፡ ፫ ፭ ።
ይህንንም ልትሠሩ አትድፈሩ አትታበዩ በሁሉ ባል ፮
ንጀሮቻችሁን አትቀሙ አስቀድሜ እንደ ነገርኋችሁ
እንደ አዳኘሁባችሁ በዚህ ሁሉ እግዚአብሔር
ፈታሒ ነውና ። ዘሌዋ፡ ፲፱ ፲፩ ።
እግዚአብሔር ለንጽሕና እንጂ ለኃጢአት አልጠራ ፯
ንምና ። ዘሌዋ፡ ፲፩ ፵፬ ። ፪ ጢሞ፡ ፩ ፱ ።
አሁንም የሚከድ ሰው መንፈስ ቅዱስን የሰጣችሁ ፰
እግዚአብሔርን እንጂ ሰውን የሚከድ እንዳይደለ
ይወቅ ። ሉቃ፡ ፲ ፲፮ ። ፩ ዮሐ፡ ፫ ፳፬ ።
ባልንጀራችሁን ስለ መውደድ ግን ልንጽፍላችሁ ፱
አትሹም እርስ በርሳችሁ እንድትዋደዱ ራሳችሁ ከእ
ግዚአብሔር የተማራችሁ ናችሁ ። ኤር፡ ፴፩ ፴፫-፴፬ ።

፲ ወከማሁ ትግበሩ ዓዲ ምስለ ኵሎሙ አኃዊክሙ እለ በኵሉ መቄዶንያ ወናስተበቍዐክሙ አኃዊነ ትብዝኁ ወትፈድፍዱ ።

፲፩ ከመ ትኩኑ የዋሃነ ወትትገበሩ ተግበረክሙ ወትትቀነዩ በእደዊክሙ ዘከመ አዘዝናክሙ ።

፲፪ ከመ ትሑሩ በኂሩት በቅድመ እለ አፍአ ወኢትጽሀቁ ወኢኀበ መኑሂ ።

ክፍል ፯፡ ዘከመ ኢይደሉ ኀዘን ዘቀቢጸ ተስፋ በእንተ እለ ሞቱ ።

፲፫ ወንፈቅድ ታእምሩ አኃዊነ በእንተ እለ ኖሙ ከመ ኢይደሉ ትትከዙ በላዕሌሆሙ ከመ ኵሉ ሰብእ እለ ቀቢጻን ተስፋሆሙ ።

፲፬ ወእምከመሰ ንትአመን ከመ ሞተ ክርስቶስ ወተንሥአ ከማሁ ያንሥኦሙ እግዚአብሔር ለምዉታን በኢየሱስ ወያመጽኦሙ ምስሌሁ ።

፲፭ ወዘንተ ንነግረክሙ በቃለ እግዚአብሔር ንሕነ ሕያዋን እለ ንተርፍ አመ ምጽአተ እግዚእነ ኢንበጽሖሙ ለሙታን ።

፲፮ እስመ ይኤዝዝ እግዚእነ ምስለ ቃለ ሊቀ መላእክት ወንፍሐተ ቀርን ዘእግዚአብሔር ዘይወርድ እምሰማይ ወይትነሥኡ ምዉታን መቅድመ እለ ሞቱ በሃይማኖተ ክርስቶስ ።

፲፯ ወእምዝ ንሕነ ሕያዋን እለ ንተርፍ ንትመሠጥ በደመና ምስሌሆሙ ኅቡረ ከመ ንትቀበሎ ለእግዚእነ ውስተ አየር ወንሄሉ እንከ ዘልፈ ኀበ እግዚእነ ።

፲፰ ወይእዜኒ መሀሩ ቢጻክሙ ዘንተ ነገረ ።

ምዕራፍ ፭፤

ክፍል ፰፡ በእንተ ነገረ ምጽአት ።

፩ ወበእንተሰ ዕድሜሁ ወዕለቱ ወጊዜሁ አኃዊነ ኢትፈቅዱ ንጽሐፍ ለክሙ ።

፪ ለሊክሙ ተአምሩ ጥዩቀ ከመ ዕለተ እግዚእነ ትመጽእ ከመ ምጽአተ ሰራቂ ሌሊተ ።

፫ አመ ይብሉ እለ ይከሕዱ ኪያሁ ከመ ውስተ ዳኅን ወሰላም እሙንቱ ወሀየ ግብተ ይመጽኦሙ ተሠርዎ ከመ ዕንስት እንተ ይመጽኣ ማሕምም ወኢይክሉ አምስጦ ።

፬ ወአንትሙሰ አኃዊነ ኢሀለውክሙ ውስተ ጽልመት ከመ ይርከብክሙ ውእቱ ዕለት ከመ ሰራቂ ።

፭ እስመ ኵልክሙ ውሉደ ብርሃን አንትሙ ወውሉደ መዓልት ወኢኮንክሙ ውሉደ ሌሊት ወኢ ውሉደ ጽልመት ።

፮ ወኢንኑም እንከ ከመ እልኩ አላ ንንቃሕ በሐሊናነ ወንትጋሕ ወንጠበብ ።



ደግሞ በመቄዶንያ ሁሉ ካሉት ወንድሞቻችሁም ፲
ጋር እንዲሁ እንድታደርጉ ወንድሞቻችን በፍቅር
ፈጽማችሁ እንድትበዙ እንማልዳችኋለን ።
ቅኖች ትሆኑ ዘንድ ሥራችሁንም ትሠሩ ዘንድ እንደ ፲፩
አዘዝናችሁ በእጃችሁ ትሠሩ ዘንድ ። ፪ ተሰ፡ ፫ ፰-፲፪።
ከሃይማኖት አፍአ ባሉ ሰዎች ፊት በቅንነት ትኖሩ ፲፪
ዘንድ ከማንም ከማን አትፈልጉ ። ሮሜ ፲፫ ፲፫ ።

ክፍል ፯፡ ስለ ሞቱ ሰዎች የቀቢጸ ተስፋ ኃዘን እንደማይገባ ።

ወንድሞቻችን! ስለ ሞቱ ሰዎች ተስፋ እንደሌላ ፲፫
ቸው ሰዎች ሁሉ ልታዝኑ እንደማይገባ ታውቁ
ዘንድ እንወዳለን ። ዘሌዋ፡ ፲፱ ፳፰፤ ዘዳ፡ ፲፬ ፩-፪ ።
ክርስቶስ ሙቶ እንደ ተነሣ ካመን እንዲሁ እግዚአ ፲፬
ብሔር ሙታንን በኢየሱስ ያስነሣቸዋል ከእርሱም
ጋር ያመጣቸዋል ። ሮሜ ፲፬ ፱፡ ፩ ቆሮ ፲፭ ፫ - ፬።
ይህንም በእግዚአብሔር ቃል እንነግራችኋለን ፲፭
ከሞት የምንቀረው እኛ ጌታችን በመጣ ጊዜ ሙታ
ንን እንቀድማቸውም ። ፩ ቆሮ፡ ፲፭ ፶፫ - ፶፩ ።
ጌታችን በመላእክት አለቃ ቃል ከሰማይ በሚወርድ ፲፮
በእግዚአብሔር መለከት ድምፅ ንቃሕ መዋቲ ብሎ
ይዘልና፡ መጀመሪያ በክርስቶስ አምነው የሞቱ
ሙታን ይነሣሉ ። ፩ ቆሮ፡ ፲፭ ፶፫ - ፶፪ ።
ከዚህ በኋላ ከሞት የምንቀረው እኛ ከነሱ ጋራ ፲፯
አንድ ሆነን ጌታችንን በአየር ላይ እንቀበለው ዘንድ
በደመና እንቀበለዋለን ከዚያ ወዲያ ለዘለዓለሙ ከጌ
ታችን ዘንድ እንኖራለን ። ዮሐ፡ ፲፪ ፳፮፤ ፲፯ - ፳፬ ።
አሁንም ይህን ነገር ለወንድሞቻችሁ አስተምሩ ። ፲፰

ምዕራፍ ፭ ።

ክፍል ፰፡ የምጽአት ነገር ስለሚናገር ።

ወንድሞቻችን! የዘመኑን የቀኑን የጊዜውን ነገር ፩
ግን ልንጽፍላችሁ አትሹም ። ማቴ፡ ፳፬ ፴፮ ።
የሌብ አመጣጥ በሌሊት እንደሆነ የጌታም ቀን እንዲሁ ፪
እንድትመጣ እናንተ ራሳችሁ ፈጽማችሁ ታውቃላ
ችሁ ። ማቴ፡ ፳፬ ፵፪ - ፵፬ ። ፪ ጴጥ፡ ፫ ፲ ።
እሱን ከሚክዱ ሰዎች በሰላምና በደኅንነት አለን ፫
በሚሉበት ጊዜ ምጥ እንደሚመጣባት ሴት ድንገት
መነቀል ይደርስባቸዋል ሊያመልጡም አይችሉም ።
ኢሳ፡ ፲፫ ፯ ። ኤር፡ ፮ ፲፬፤ ፰ ፲፩ ።
ወንድሞቻችን! እናንተስ ያ ቀን እንደ ሌባ ያገኛችሁ ፬
ዘንድ በጨለማ ውስጥ አይደላችሁም ። ኤፌ ፭ ፰ ።
ሁላችሁ የብርሃን ልጆች የቀን ልጆች ናችሁ እንጂ ፭
እንጂ የሌሊት ልጆች የጨለማ ልጆችም አይደላች
ሁምና ። ሮሜ ፲፫ ፲፪ ። ኤፌ ፭ ፱ ።
እንግዲህ እንደነዚያ አናንቀላፋ በአሳባችን እንንቃ ፮
እንትጋ እንራቀቅ እንጂ ።

፯ እስመ እለ ይነውሙ ሌሊተ ይነውሙ ወእለሂ ይሰ
ክሩ ሌሊተ ይሰክሩ ።
፰ ወንሕነሰ እንዘ ውሉደ መዓልት ንሕነ ንንቃሕ ወን
ልበስ ልብሰ ኃጺን ዘሃይማኖት ወዘተፋቅሮ ወንትቀ
ጸል ጌራ ተስፋ መድኃኒት ።
፱ እስመ ኢረሰየነ እግዚአብሔር ለመንሱት ዘእንበለ
ለሕይወት ወመድኃኒት በእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ፣
፲ ዘሞተ ለነ ቤዛነ እመኒ ንቁሐን ንሕነ ወእመኒ ንው
ማን ምስሌሁ ነሐዩ ኩልነ ።

ክፍል ፰ ፡ ዘከመ ይደሉ ጸልዮ ለአኃው ።

፲፩ ወይእዜኒ አስተፍሥሑ ቢጸክሙ በእንተዝ ወይሕ
ንጽ አሐዱ ክልአ ዘከመ ትገብሩ ዓዲ ።
፲፪ ወናስተበቍዐክሙ አኃዊነ ዑቅዎሙ ለእለ ይጻምዉ
በውስቴትክሙ ወለእለ ይቀውሙ ለክሙ በእንተ
እግዚእነ ወይሜህሩክሙ ።
፲፫ ወአክብርዎሙ ፈድፋደ ወአፍቅርዎሙ በእንተ ምግ
ባሮሙ ወተአምኅዎሙ ።
፲፬ ወናስተበቍዐክሙ አኃዊነ ገሥፅዎሙ ለዝሉፋን ናዝ
ዝዎሙ ለኀዙናን ፡ ፁርዎሙ ለድኩማን ፡ ወተዐገሡ
ላዕለ ኵሉ ።
፲፭ ዑቁ ኢትግበሩ እኩየ ህየንተ እኪት አላ ተበደሩ
ዘልፈ ለሠናይ በበይናቲክሙ ወበኵሉሂ ።
፲፮ ተፈሥሑ በኵሉ ጊዜ ወጸልዩ ወትረ ።
፲፯ አእኵትዎ ለእግዚአብሔር አብ በእንተ ኵሉ ግብር።
፲፰ እስመ ዝውእቱ ፈቃዱ ለእግዚአብሔር እምውስቴ
ትክሙ በኢየሱስ ክርስቶስ ።
፲፱ መንፈሰ ኢታጥፍኡ ።
፳ ወተነብዮ ኢትመንኑ ።
፳፩ ወኵሎ አመክሩ ወዘሠናይ አፅንዑ ።
፳፪ ወተገኀሡ እምኵሉ ምግባር እኩይ ።
፳፫ ወእግዚአብሔር አምላክ ሰላም ይቀድስክሙ ፍጹመ
ወያጥዒክሙ ነፍሰክሙ ወመንፈሰክሙ ወሥጋክሙ
በንጽሕ እስከ ምጽአተ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ።
፳፬ ወዘጸውዐክሙ ጻድቅ ውእቱ ይግበር ለክሙ ዘንተ።
፳፭ ኦ አኃዊነ ጸልዩ ለነ ።
፳፮ አምኁ ኵሎ አኃዊነ በአምኃ ቅድሳት ወተአምኁ
በበይናቲክሙ ።



የሚያንቀላፉ ሌሊት ያንቀላፋሉ የሚሰክሩም ሌሊት ፯
ይሰክራሉና ። ሉቃ ፳፩ ፴፬ ።
እኛ ግን የቀን ልጆች እንደመሆናችን እንንቃ የሃይ ፰
ማኖትና የፍቅር የጥሩር ልብስ እንልበስ ተስፋ ያለ
በትን የመዳን ራር ቊር እንቀዳጅ ። ኢሳ ፶፱ ፲፯ ።
እግዚአብሔር በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ለሕይ ፱
ወት ለደኅንነት እንጂ ለጥፋት አልፈጠረንምና ።
ሮሚ ፱ ፳፪ ።
ቤዛ ሆኖ የሞተልን እሱ ነው ፣ ብንነቃም ብናንቀላ ፲
ፋም ሁላችን ከርሱ ጋር እንኖራለን ። ሮሚ ፲፬ ፰-፱ ።

ክፍል ፰ ፡ ለወንድሞቻችን መጸለይ ስለ ሚገባ ።

አሁንም ስለዚህ ወንድሞቻችሁን ደስ አሰኙ ፣ ደግ ፲፩
ሞም እንደምታደርጉት አንዱ አንዱን ይነፀው ።
ዕብ ፲ ፳፬ - ፳፭ ።
ወንድሞቻችን! በመከከላችሁ የሚደክሙትን ስለ ፲፪
ጌታችንም የሚቆሙላችሁን የሚያስተምሯችሁን
ዕወቁአቸው ብለን እንማልዳችኋለን ። ፩ ቆሮ ፲፮ ፲፰ ።
በበጎ ሥራቸውም ምስሏቸው ፣ እጅግም ውደዷ ፲፫
ቸው አክብሯቸውም ።
ወንድሞቻችንን እንማልዳችኋለን! ደፋሮችን ገሥጿ ፲፬
ቸው ያዘኑት ፣ አፅናኑዋቸው ፣ የደከሙትን አፅኑአ
ቸው ሁሉንም ታገሡ ። ፪ ተሰ ፫ ፲፭ ።
ተጠንቀቁ በክፉ ፈንታ ክፉ አታድርጉ ዘወትር ፲፭
እርስ በራሳችሁም ሆነ ለሌላው መልካም ነገር
ትሠሩ ዘንድ ተሽቀዳደሙ እንጂ ። ዘሌዋ ፲፱ ፲፰ ።
ሁል ጊዜ ደስ ይበላችሁ ዘወትርም ጸልዩ ። ፲፮
ስለ ሥራው ሁሉ እግዚአብሔር አብን አመስግኑት ። ፲፯
ሉቃ ፲፰ ፩ ። ሮሚ ፲፪ ፲፪ ። ቈላ ፬ ፪ ።
ከናንተ ዘንድ እግዚአብሔር የሚሻው ይህ ነውና ፲፰
በኢየሱስ ክርስቶስ ስለ ተደረገላችሁ አመስግኑት ።
ልባችሁ አታበክኑ ። ኢሳ ፷፫ ፲ ። ፩ ቆሮ ፲፬ ፴ - ፴፱ ። ፲፱
ትንቢትን አትናቁ ። ፩ ቆሮ ፲፬ ፩ ። ፳
ሁሉንም መርምራችሁ በጎ በጎውን ያዙ ። ሮሚ ፪ ፲፰። ፳፩
ከክፉ ነገር ሁሉ ራቁ ። ዘፀአ ፳፫ ፯ ። ፳፪
የሰላም አምላክ እግዚአብሔር ፈጽሞ ያክብራችሁ ፳፫
ነፍሳችሁን ልቡናችሁን ሥጋችሁን ጌታችን ኢየ
ሱስ ክርስቶስ እስከሚመጣበት ቀን ድረስ ይጠብቃ
ላችሁ ። ሮሚ ፲፭ ፴፫ ።
የጠራችሁም ይህን ያደርግላችሁ ዘንድ እውነተኛ ፳፬
ነው ። ፩ ቆሮ ፩ ፱ ። ፲ ፲፫ ። ፪ ተሰ ፫ ፫ ።
ወንድሞቻችን! ጸልዩልን ። ቈላ ፬ ፫ ። ፳፭
ወንድሞቻችንን ሁሉ በተቀደሰ ሰላምታ ቸር አላች ፳፮
ሁን? በሉ ፣ እርስ በርሳችሁ ቸር አላችሁ? ተባባሉ ።
ሮሚ ፲፮ ፲፮ ።

፳፯ አምሕለክሙ በእግዚእነ ታንብብዋ ለዛቲ መጽሐፍ
ላዕለ ኵሎሙ አኀዊነ ቅዱሳን ።
፳፰ ጸጋሁ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ምስሌክሙ
አሜን ።

ተፈጸመ መልእክት ቀዳማዊ ኀበ ሰብአ ተሰሎንቄ ወተጽሕፈ በአቴና ወተፈነወ ምስለ ጢሞቴዎስ ወስልዋኖስ ።

ወስብሐት ለእግዚአብሔር አሜን ።



ይህችን መጽሐፍ ለምእመናን ወንድሞቻችን ሁሉ ፳፯
ታነቧት ዘንድ በጌታችን ስም አማፅናችኋለሁ ።
የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ጸጋ ከእናንተ ጋር ፳፰
ይሁን ፤ አሜን ። ሮሜ ፲፮ ፳ - ፳፬ ። ፊልጵ ፬ ፳፫ ።

በአቴና ተጽፎ በጢሞቴዎስና በስልዋኖስ እጅ መጀመሪያ ወደ ተሰሎንቄ ሰዎች የተላከው መልእክት ተፈጸመ ።

ለእግዚአብሔር ምስጋና ይሁን ፤ አሜን ።



## ኀበ ሰብአ ተሰሎንቄ ፪።

### ምዕራፍ ፩፤

#### ክፍል ፩፤ በእንተ ተመክሖ በእንተ ፍቅረ አኀው ።

፩ እምጳውሎስ ወስልዋኖስ ወጢሞቴዎስ ለቤተ ክርስ
ቲያን ዘተሰሎንቄ ምእመናን በእግዚአብሔር አቡነ
ወእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ።
፪ ሰላም ለክሙ ወጸጋ እግዚአብሔር አቡነ ወእግዚእነ
ኢየሱስ ክርስቶስ ።

፫ ርቱዕ ናእኵቶ ለእግዚአብሔር በኵሉ ጊዜ በእንቲ
አክሙ አኀዊነ በከመ ይደልዎ እስመ ዐብየት ሃይማ
ኖትክሙ ወፈድፈደት ተፋቅሮትክሙ ምስለ ኵሉ
ቢጽክሙ ።
፬ ከመ ንሕነኒ ንትመካሕ ብክሙ በቤተ ክርስቲያኑ
ለእግዚአብሔር በእንተ ሃይማኖትክሙ ወትዕግሥት
ክሙ በሕማምክሙ ወምንዳቤክሙ ዘትትዔገሡ
ወትትዌከፉ ።
፭ ከመ ታርእዩ ኵነኔ ጽድቁ ለእግዚአብሔር ከመ ይክ
ፍልክሙ መንግሥቶ ዘበእንቲአሁ ተሐምሙ ።

፮ ወርቱዕሰ ይትፈደዩ በኀበ እግዚአብሔር ሕማመ እለ
ያሐምሙክሙ ።
፯ ወለክሙ ለእለ ተሐምሙ ዕረፍት ምስሌነ በምጽአቱ
ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ እምሰማያት ምስለ
መላእክተ ኃይሉ ።

፰ ከመ ይትበቀሎሙ በነደ እሳት ለእለ ኢየአምርዎ
ለእግዚአብሔር ወለእለ ኢይሰምዑ ትምህርተ ወን
ጌሉ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ።
፱ ወይረክቡ ፍዳሆሙ ኵነኔ ኀጕል ወተሠርዎ ዘለዓ
ለም እምቅድመ ገጹ ለእግዚእነ ወእምስብሐተ
ኃይሉ ።
፲ አመ ይመጽእ ይሴባሕ በቅዱሳኒሁ ወይትአኰት በእለ
የአምኑ ቦቱ እስመ ይትአመነነ ስምዕነ በላዕሌክሙ
በይእቲ ዕለት ።
፲፩ በእንተዝ እጼሊ ዘልፈ በእንቲአክሙ ከመ ይክፍል
ክሙ ርስቶ ዘጸውዐክሙ እግዚአብሔር ወይፈጽም
ለክሙ ኵሎ ሣህሎ ወሠናይቶ ወምግባረ ሃይማኖት
በኃይሉ ።
፲፪ ከመ ይሰባሕ ስሙ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ በላ
ዕሌክሙ ወአንትሙሂ ቦቱ ወበከመ ጸጋሁ ለአምላ
ክነ ወእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወአንትሙሂ ተሀ
ልዉ ቦቱ ።

## ወደ ተሰሎንቄ ሰዎች ፪።

### ምዕራፍ ፩።

#### ክፍል ፩፡ በወንድሞች መፋቀር ስለ መመካት ።

ከጳውሎስ ከስልዋኖስና ከጢሞቴዎስ በአባታችን ፩
በእግዚአብሔር በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ አም
ነው በተሰሎንቄ ላሉ ምእመናን ትድረስ ።
ሰላም ለእናንተ ይሁን፤ የአባታችን የእግዚአብሔር ፪
የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ጸጋ ይደረግላችሁ ።
፩ ቆሮ ፩ ፫ ። ቈላ ፩ ፪ ።
ወንድሞቻችን! የሚገባው እንደ መሆኑ ስለ እናንተ ፫
ዘወትር እግዚአብሔርን ልናመሰግነው ይገባል፤ ሃይ
ማኖታችሁ ፀንታለችና ከወንድሞቻችሁ ሁሉ ጋራም
ፍቅራችሁ በዝታለችና ። ኢዮ ፲፯ ፱ ።
እኛም ታግሣችሁ ስለምትቀበሉት መከራችሁና ፬
ሥቃያችሁ በእግዚአብሔር ቤተ ክርስቲያን ፊት
እንመካባችሁ ዘንድ ። ፪ ቆሮ ፯ ፲፬ ።

የእግዚአብሔርን እውነተኛ ፍርዱን ትገልጹ ዘንድ ፭
ስለሱ መከራ የምትቀበሉለት መንግሥቱን ያድላ
ችሁ ዘንድ ። መዝ ፱ ፯ - ፰ ።
መከራ የሚያፀኑባችሁ ግን በእግዚአብሔር ዘንድ ፮
ፍዳቸውን ሊቀበሉ ይገባል ። ራእ ዮሐ ፮ ፲ ።
መከራ ለምትቀበሉ ለእናንተስ ጌታችን ኢየሱስ ክር ፯
ስቶስ ከሀሊነቱን የሚገልጥባቸው መላእክትን አስከ
ትሎ በመጣ ጊዜ ከእኛ ጋራ ዕረፍት አላችሁ። ማቴ
፳፭ ፴፩ ራእ ዮሐ። ፲፬ ፲፫ ።
እግዚአብሔርን በማያውቁት የጌታችን ኢየሱስ ክር ፰
ስቶስ የወንጌሉን ትምህርት የማይሰሙትን በሚያ
ቃጥል እሳት ይበቀላቸው ዘንድ ። ዕብ፡ ፲ ፳፯ ።
ከጌታችን ፊትና ከከሀሊነቱ ጌትነትም የተነሣ ብድ ፱
ራቸውን የጥፋት ፍዳቸውንና የዘለዓለም መነቀልን
ያገኛሉ ። ዘዳግ፡ ፴፫ ፪፤ ኢሳ፡ ፪ ፲ - ፲፱ ።
በቅዱሳኑ ይገለጽ ዘንድ በሚያምኑበትም ይመሰ ፲
ገን ዘንድ በመጣ ጊዜ በዚያች ቀን ስለ እናንተ የመ
ሰከርነው ምስክርነታችን ይታመንልናልና። ቈላ ፫ ፬።
ስለዚህም ሁል ጊዜ ስለ እናንተ እጸልያለሁ እግዚ ፲፩
አብሔር እናንተን የጠራለት ርስቱን ያድላችሁ
ዘንድ ይቅርታውንና ቸርነቱን ሁሉ በከሀሊነቱ አምና
ችሁ በምትሠሩበት ሥራ ይፈጽምላችሁ ዘንድ ።
የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ስም በእናንተ ይገለጽ ፲፪
ዘንድ እናንተም በእሱ ትፀኑ ዘንድ ፈጣሪያችን ጌታ
ችን ኢየሱስ ክርስቶስ እንደሚያደርግላችሁ ቸርነት
መጠን፤ እናንተም በእሱ አምናችሁ ትኖሩ ዘንድ ።

ምዕራፍ ፪ ፤

<u>ክፍል ፪ ፡ በእንተ ምጽአቱ ለእግዚእነ ።</u>

፩ ንነግረክሙ አኀዊነ በእንተ ምጽአተ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ።

፪ ወአንትሙኒ ውስተ ማኅበሩ ዑቁ ወኢያደንግፁክሙ ፍጡነ ወኢትትሀወኩ እምአእምሮ ኢ በመንፈስ ወኢ በነገር ወኢ በመጽሐፍ ከመ ዘእምኀቤነ ለአመ ትመጽእ ዕለተ እግዚእነ ።

፫ አልቦ ዘያስሕተክሙ ወኢ በምንትኒ እስመ ኢትመጽእ ይእቲ ዕለት ለእመ ኢቀደመ መጺአ ዘየሀውክ ወይትከሠት ብእሴ ዐመፃ ወልደ ሕርትምና ።

፬ ዐላዊ ወሐሳዊ ዘያዐቢ ርእሶ ወይብል ለኵሉ አነ ውእቱ እግዚአብሔር አምላክ ወይነብር በቤተ እግዚአብሔር ወይሬሲ ርእሶ ከመ እግዚአብሔር ።

፭ ኢትዜከሩኑ ከመ አመ ሀሎኩ ኀቤክሙ አቅደምኩ ወነገርኩክሙ ዘንተ ።

፮ ወይእዜኒ ተአምሩ ዘይከልአ አስተርእዮ እስከ ይበጽሕ ዕድሜሁ ።

፯ እስመ እከየ ምክረ ኃጢአት ወድአ ይትገበር በላዕሌሁ ፡ ወዳእሙ ይእዜሰ እኁዝ እስከ ይትኀደግ እማእከል ።

፰ ወይእተ አሚረ ይትከሠት ወልደ ዐመፃ ኃጥእ ዘሀለዎ ያጥፍኦ መንፈሱ ለእግዚእነ ኢየሱስ ወይስዕሮ በአስተርእዮተ ምጽአቱ ።

፱ ወምጽአቱሰ ለዝንቱ በኃይለ ሰይጣን በኵሉ ኃይል ወትእምርት ወመንክር ዘሐሰት ።

፲ ወበኵሉ አስሕቶ ዘኃጢአት ለሕርቱማን እስመ ኢተወክፉ ፍቅረ ቃለ ጽድቅ በዘየሐይዉ ።

፲፩ ወበእንተዝ ይፌኑ ሎሙ እግዚአብሔር ኃይለ መስሕተ ከመ ይእመኑ በሐሰት ።

፲፪ ከመ ይትኰነኑ ኵሎሙ እለ ኢየአምሩ በጽድቅ ወየኀብሩ በዐመፃ ።

፲፫ ወንሕነሰ አኀዊነ ርቱዕ ናእኵቶ ለእግዚአብሔር ዘልፈ በእንቲአክሙ እለ አፍቀረክሙ እግዚአብሔር እስመ ኃረየክሙ ወተሣሃለክሙ እግዚአብሔር ርእሰ ሕይወት በተቀድሶ መንፈስ ወበሃይማኖተ ጽድቅ ።

፲፬ ዘበእንቲአሁ ጸውዐክሙ በትምህርተ ወንጌል ከመ ትሕየዉ በስብሐቲሁ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ።

፲፭ ወይእዜኒ አኀዊነ ቁሙ ወዕቀቡ ትእዛዘ ዘመሀሩክሙ ወሠርዑክሙ ዘበቃልነ ወዘበመጽሐፍነ ።

ምዕራፍ ፪ ።

<u>ክፍል ፪ ፡ ስለ ጌታችን መምጣት ።</u>

ወንድሞቻችን ! ስለ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ መምጣት እንነግራችኋለን ። ማቴ፡ ፳፬ ፴፩ ። ፩

በአንድነቱ ውስጥ ያላችሁ እናንተም ዕወቁ፡ አሁን ይመጣል ብለው አያስደንግጧችሁ ፡ ከዕውቀት ወጥታችሁ አትሸበሩ፡ መንፈስ ቅዱስ አናገረን ቢሉ እንደበት አሰላን ቢሉ መጽሐፍን ቢጽፉ አትሸበሩ። ፪

በምንም በምን የሚያስታችሁ አይኑር ሕዝብን የሚያውከው (ሐሳዌ መሲሕ) ከመምጣቱ በፊት ያች ቀን አትመጣምና የዐመፅ ሰው በኃጢአት የተወለደው መጥቶ ካልተገለጠ ። ኢሳ፡ ፴፯ ፳፫ ፡ ዳን፡ ፯ ፳፭ ። ፫

ወንጀለኛ ራሱን ከፍ ከፍ የሚያደርግ ለሁሉም እኔ እግዚአብሔር አምላክ ነኝ የሚል ራሱን እንደ እግዚአብሔር አድርጎ በእግዚአብሔር ቤት የሚቀመጥ። ኢሳ፡ ፲፬ ፲፫ ፡ ዳን፡ ፲፩ ፴፯ ። ራእዮ ሐ፡ ፲፫ ፮ ። ፬

ከእናንተ ዘንድ በነበርኩ ጊዜ አስቀድሜ ይህን እንደ ነገርኳችሁ አታስቡምን ? ። ፭

አሁንም ከመታየት የሚከለክለው ጊዜ እስኪደርስ እንደሆነ ታውቃላችሁ ። ፮

የኃጢአት ተንኰል ትምህርት በርሱ ላይ ፈጽሞ ይደረጋልና ዛሬ ግን በመካከል እስኪጣል ድረስ ተገቷል ። ግብ፡ ሐዋ፡ ፳ ፳፱ ። ፩ ዮሐ፡ ፬ ፫ ። ፯

ያን ጊዜም የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ሥልጣኑ ያጠፋው ዘንድ ያለው በመምጣቱም መገለጽ የሚያሳልፈውን ኃጥእ የዓመፅ ልጅ ይገለጣል። ኢዮ፡ ፬ ፱። ፰

የሱም አመጣጡ በሰይጣን ኃይል ነው ብዙ ምትሐትን በማሳየት ተአምራትን በማድረግ ሐሰት የሆነ ድንቅ ድንቅ ሥራን ይሠራል። ማቴ፡ ፳፬ ፳፬ ። ፱

ለጐሰቈሉ ኃጢአትን በሚያስተምር በፍጹም ማሳት ይመጣል በሚድኑ ገንዘብ የእውነትን ቃል ፍቅርን አልተቀበሉምና ። ፪ ቆሮ፡ ፪ ፡ ፲፭ ። ፬ ፫ ። ፲

ስለዚህም በሐሰት ያምኑ ዘንድ እግዚአብሔር የሚያስት ተአምራት ያዝዝባቸዋል ። ፩ ነገሥ፡ ፳፪ ፳፪ ፤ ሕዝ፡ ፲፬ ፱፡ ሮሜ ፩ ፳፬ ። ፲፩

በእውነት የሚያምኑ በዓመፅ የሚተባበሩ ሁሉ ይፈረድባቸው ዘንድ ። ሕዝ፡ ፳ ፳፬ - ፳፭ ። ፲፪

ወንድሞቻችን! እኛስ እግዚአብሔር ስለሚወዳችሁ ስለ እናንተ ዘወትር እግዚአብሔርን ልናመሰግነው ይገባል ፡ የሕይወት መገኛ እግዚአብሔር በመንፈስ ቅዱስ ቅድስና በእውነተኛ ሃይማኖትም መርጦአችኋል ይቅር ብሎአችኋልና ። ኤፌ፡ ፩ ፬ ። ፲፫

በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ክብር ትድኑ ዘንድ በወንጌል ትምህርት እናንተን የጠራችሁ ። ፲፬

አሁንም ወንድሞቻችን! ፀኑ ከቃላችን አግኝተው በመጽሐፋችን የጻፍነውን ጠቅሰው ያስተማሯችሁን ትእዛዝ ጠብቁ ። ምዕ፡ ፫ ፮ ። ፲፭

፲፮ ወውእቱ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወእግዚአብ
ሔር አቡነ ዘአፍቀረነ ወወሀበነ ፍሥሐ ዘለዓለም
ወተስፋ ሠናየ በጸጋሁ ።
፲፯ ውእቱ ያስተፍሥሕክሙ ልበክሙ ወያፅንዕክሙ
በኵሉ ምግባር ወበኵሉ ቃል ሠናይ ።

## ምዕራፍ ፫ ፤

### ክፍል ፫ ፡ ዘከመ ይደሉ ጸልዮ እምድኅነተ ሰብአ እኩያን ።

፩ ወይእዜኒ አኀዊነ ጸልዩ ለነ ከመ ይሩጽ ቃለ እግዚ
አብሔር ወይሰባሕ በከመ በኀቤክሙ ።

፪ ወከመ ንድኃን እምሰብእ እኩያን ወዐላውያን እስመ
አኮ ኵሉ ዘየአምን ።
፫ ወእግዚአብሔርሰ ምእመን ወጻድቅ ዘያጸንዐክሙ
ወየዐቅበክሙ እምኵሉ እኩይ ።

፬ ንትአመነክሙ ምስለ እግዚአብሔር ከመ ትግበሩ
ዘአዘዝናክሙ ወገበርክሙሂ ።

፭ ወእግዚእነ ያርትዕ ልበክሙ ውስተ ፍቅረ እግዚ
አብሔር ወውስተ ተስፋሁ ለክርስቶስ ።

### ክፍል ፬ ፡ ዘከመ ይደሉ በሊዐ በተቀንዮ ።

፮ አኀዊነ ንኤዝዘክሙ በስመ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስ
ቶስ ተገኃሥዎሙ ለኵሎሙ቟ ቢጽ እለ የሐውሩ በት
ምይንት ወአኮ በሥርዐት ዘሠራዕናሆሙ ።

፯ ለሊክሙ ተአምሩ ከመ ርቱዕ ትትመሰሉነ ከመ
ኢሰሳዕነ ላዕሌክሙ ።

፰ ወኢበላዕነ እክለ ባዕድ በከንቱ ዘእንበለ ዳእሙ ወን
ሠርሕ መዓልተ ወሌሊተ ወንትጌበር ከመ ኢናክ
ብድ ላዕሌክሙ ።
፱ ወአኮሰ ዘኢኮነ ብዉሐነ ዳእሙ አርአያ ከመ ንኩን
ክሙ ከመ አንትሙ ትትመሰሉነ ።

፲ ወአመሂ ሀለውኩ ኀቤክሙ ዘንተ አዘዝኩክሙ ዘኢ
ይፈቅድ ይትቀነይ ኢይሴሰይ ።
፲፩ ሰማዕነ ከመ ቦ እምውስቴትክሙ እለ የሐውሩ በሁ
ከት ወአልቦ ዘይትቀነዩ ዓዲ መስተሐውራን ።

፲፪ ወለእለ ከመዝ ንኤዝዞሙ ወንጌሥፆሙ በስሙ ለእግ
ዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ከመ በየውሃት ወበጽምው
ይትገበሩ ተግባሮሙ ወይሴሰዩ ሲሳዮሙ ።
፲፫ ወአንትሙሂ አኀዊነ ኢትትሀከዩ ገቢረ ሠናይ ኵሎ
ጊዜ ።

ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ፡ በቸርነቱ የወደደን ፲፮
የዘለዓለም ደስታንና እውነተኛ ተስፋን የሰጠን አባ
ታችን እግዚአብሔር እሱ ። ፩ ዮሐ፡ ፬ ፲ ።
ጸጋውን ሰጥቶ ልባችሁን ደስ ያሰኛችሁ በፍጹም ፲፯
ምግባር በበጎ አነጋገር ያጽናችሁ ። ፩ ተሰ፡ ፫ ፲፫ ።

## ም ዕ ራ ፍ ፫ ።

### ክፍል ፫ ፡ ከክፉ ሰዎች ለመዳን መጸለይ እንዲገባ ።

አሁንም ወንድሞቻችን! የእግዚአብሔር ቃል ከእና ፩
ንተ እንደ ደረሰ እንዲሁ ከሁሉ ዘንድ እንዲደርስ
ጸልዩልን ። ቈላ፡ ፬ ፫ ።
ከክፉ ሰዎችና ከከሐዲዎች እንድን ዘንድ፡ ሁሉ በእ ፪
ግዚአብሔር የሚያምን አይደለምና ።
ከክፉ ሁሉ የሚጠብቃችሁና የሚያፀናችሁ እግዚ ፫
አብሔር ግን የታመነ እውነተኛ አምላክ ነው ።
ማቴ፡ ፮ ፲፫፡ ፩ ቆሮ፡ ፩ ፱፡ ፲ - ፲፫ ።
ከእግዚአብሔር ጋር ያዘዝናችሁን እንደምታደርጉ ፬
እንታመንባችኋለን ከዚህ በፊትም አድርጋችኋል ።
፪ ቆሮ፡ ፯ ፲፮፡ ገላ፡ ፭ ፲ ።
ጌታችንም ልቡናችሁን እግዚአብሔርን ወደ መው ፭
ደድና ወደ ክርስቶስ ተስፋ ያቅናው። ፩ ነገ፡ ፰ ፶፰።

### ክፍል ፬፡ ሠርቶ መብላት ስለሚገባ ።

ወንድሞቻችን! በሠራንላቸው ሥርዓት ያይደለ በተ ፮
ንኰል የሚሄዱትን ሰዎች ሁሉ ተለዩዋቸው ብለን
በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ እናዝዛችኋለን ።
ማቴ፡ ፲፰ ፲፯፡ ሮሜ ፲፯ ፲፯፡ ቲቶ፡ ፫ ፲ ።
እኛ በእናንተ ላይ እንዳልሰሳን ሁሉ እናንተም እኛን ፯
ትመስሉን እንዲገባ እናንተ ራሳችሁ ታውቃላችሁ ።
፩ ቆሮ፡ ፬ ፲፮፡ ፩ ተሰ፡ ፩ ፮ ።
እናንተን እንዳናስቸግር በመዓልትም በሌሊትም ፰
ሠርተን የደከምንበትን እንጂ የሌላውን እህል በከ
ንቱ አልበላንም ። ፩ ቆሮ፡ ፬ ፲፪ ።
ግን የማይገባን ሆኖ አይደለም እናንተ ትመስሉን ፱
ዘንድ አብነት እንድንሆናችሁ ነው እንጂ። ማቴ ፲ ፲፡
፩ ቆሮ፡ ፬ ፲፮ ።
ከእናንተም ዘንድ በነበርኩ ጊዜ ይህን አዝዣችኋለሁ ፲
ሊሠራ የማይወድ አይብላ ብዬ ። ዘፍ፡ ፫ ፲፱ ።
በመካከላችሁ በማወክ የሚኖሩ የሚሠሩት የሌላቸው ፲፩
በዚያውም ላይ ነገር አዋሳጆች እንዳሉ ሰምተናል ።
ኢሳ፡ ፶፮ ፲ ።
እንደነዚህ ያሉትን በቅንነት በፀጥታ እየሠሩ ምግብ ፲፪
ቸውን እንዲመገቡ በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ
ስም እንመክራቸዋለን እናዝዛቸዋለን ። ሮሜ ፲፪ ፲፩።
ወንድሞቻችን! እናንተም ሁል ጊዜ በጎ ሥራ መሥ ፲፫
ራትን ቸል አትበሉ ። ገላ፡ ፮ ፱ ።

## ኀበ ሰብአ ተሰሎንቄ ፪ ።

፲፬ ወእመቦ ዘኢይትኤዘዝ ለቃልክሙ ወለመጽሐፍክሙ
ይትፈለጥ ወኢትትሀወልዎ ከመ ይትኃፈር ።
፲፭ ወከመሰ ጸላኢ ኢትረስይዎ አላ ገሥፅዎ ከመ እኁ
ክሙ ።
፲፮ ወውእቱ አምላከ ሰላም የሀብክሙ ሰላመ በኵሉ
ጊዜ ወበኵሉ ግብር ፥ ወእግዚእነ የሃሉ ምስለ ኵል
ክሙ ።
፲፯ ዘንተ አምኃ ዘጸሐፍኩ ለክሙ በእዴየ አነ ጳውሎስ፥
ወዝንቱ ትእምርትየ ውስተ ኵሉ መጻሕፍትየ ከመዝ
እጽሕፍ ።
፲፰ ጸጋሁ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ የሃሉ ምስለ
ኵልክሙ ፥ አሜን ።



ተፈጸመት ክልእት መልእክት ኀበ ሰብአ ተሰሎንቄ ወተጽሕፈት በሎዶቅያ ወተፈነወት በእደ ጢኪቆስ ።
ወስብሐት ለእግዚአብሔር ፥ አሜን ።

## ወደ ተሰሎንቄ ሰዎች ፪ ።

ለቃላችሁና ለመጽሐፋችሁ የማይታዘዝ ቢኖር ይለይ ፲፬
እንዲያፍር አትቀላቀሉት ። ማቴ፥ ፲፰ ፲፯ ።
እንደ ጠላት ግን አታድርጉት ወንድማችሁ እንደመ ፲፭
ሆኑ ምከሩት ገሥፁት እንጂ ። ዘሌ፥ ፲፱ ፲፯ ።
የሰላም አምላክ እርሱ ሁል ጊዜ በሥራው ሁሉ አን ፲፮
ድነቱን ይስጣችሁ ፥ ጌታችን ከሁላችሁ ጋር ይኑር ።
ሮሜ ፲፭ ፴፫፥ ፲፮-፳ ።
ይህን ሰላምታ በእጄ የጻፍኩላችሁ እኔ ጳውሎስ ፲፯
ነኝ፥ በመጻሕፍቶቼ ሁሉ ምልክቴ ይህ ነው እንዲህ
እጽፋለሁ ። ፩ ቆሮ፥ ፲፮ ፳፩ ።
የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ጸጋ ከሁላችሁ ጋር ፲፰
ይሁን፥ አሜን ። ፪ ጢሞ፥ ፬ ፳፪ ።



በሎዶቅያ ተጽፋ በጢኪቆስ እጅ ወደ ተሰሎንቄ ሰዎች የተላከችው ሁለተኛዪቱ መልእክት ተፈጸመች ።
ለእግዚአብሔር ምስጋና ይሁን፥ አሜን ።




ምዕራፍ ፩፡

ክፍል ፩፡ ዘከመ ኢይደሉ ዘውዐ ነገር።

፩ እምጳውሎስ ሐዋርያሁ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ
በትእዛዘ እግዚአብሔር መድኀኒነ ወኢየሱስ ክርስ
ቶስ ተስፋነ።

፪ ለጢሞቴዎስ ወልድየ ዘአፈቅር በሃይማኖት፡ ሰላም
ለከ ወሣህል ወጸጋሁ ለእግዚአብሔር አቡነ ወእግዚ
እነ ኢየሱስ ክርስቶስ።

፫ እስመ አስተብቋዕኩከ ትንበር ኤፌሶን አመ አሐ
ውር መቄዶንያ ከመ ትገሥፆሙ ከመ ኢያምጽኡ
ካልአ ትምህርተ።

፬ ወኢያምጽኡ መኃድምተ ወዘውዐ ነገር ዘይፈጥሩ
በዘያስሕቱ ወያመጽኡ ተኃሥሦ ወየኀድጉ ሕገ እግ
ዚአብሔር ዘሃይማኖት።

፭ ወማኅለቅቱሰ ለትእዛዝ ተፋቅሮ በንጹሕ ልብ፡ ወበ
ሠናይ ግእዝ፡ ወሃይማኖት ዘአልበ ኑፋቄ።

፮ እስመ ቦ እለ አውከኩ ወገብኡ ውስተ ነገረ ከንቱ።

፯ ወእንዘ ይፈቅዱ መምህራነ ይኩኑ ኢየአምሩ ዘለሊ
ሆሙ ይነብቡ።

፰ ነአምር ከመ ሠናይ ውእቱ ኦሪት ለዘይገብሮ በሕጉ።

፱ ወነአምር ዘኒ ከመ አኮ ለጻድቃን ዘይሠራዕ ሕግ
ዘእንበለ ለኃጥእን ወለጽልሕዋን ወለዝሉፋን ወለው
ፁእን እምጽድቅ ወለርኩሳነ ልብ፡ ወቀተልተ አበ
ዊሆሙ ወእሞሙ፡ ወቀተልተ አዝማዲሆሙ ወቀተ
ልተ ነፍስ።

፲ ዘማውያን ወእለ የሐውሩ ብእሲተ ብእሲ ሰረቅተ
ሰብእ፡ ሐሳውያን ወእለ ይምሕሉ በሐሰት።

፲፩ ወቦ ባዕድኒ ዓዲ በዘይትቃወምዋ ለትምህርተ ሕይ
ወት ዘወንጌለ ስብሐቲሁ ለብፁዕ እግዚአብሔር ዘአነ
ተአመንኩ በቱ።

፲፪ አአኵቶ ለዘተአመነኒ ወአጽንዐኒ በክርስቶስ ኢየ
ሱስ እግዚእነ እስመ ምእመነ ረሰየኒ ለመልእክቱ።

፲፫ እንዘ ቀዲሙ ጸራፊ አነ ወሰዳዲ ወጸአሊ፡ ወበሕቱ

ምዕራፍ ፩።

ክፍል ፩፡ ዋዛ ፈዛዛ መናገር ስለማይገባ።

መድኃኒታችን በሆነው በእግዚአብሔር አለኝታችን ፩
በሆነው በኢየሱስ ክርስቶስ ትእዛዝ የጌታችን የኢ
የሱስ ክርስቶስ ሐዋርያ ከምሆን ከእኔ ከጳውሎስ
የተላከ መልእክት። ቈላ፡ ፩ ፳፯። ቲቶ ፩ ፫።
በሃይማኖት ለምወደው ልጄ ለጢሞቴዎስ ትድረስ ፪
ሰላም ላንተ ይሁን ይቅርታም ይደረግልህ የአባታ
ችን የእግዚአብሔር የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ
ጸጋ ይደርብህ። ግብ፡ ሐዋ፡ ፲፮ ፩። ቲቶ ፩ ፱።
ወደ መቄዶንያ በሄድኩ ጊዜ በኤፌሶን እንድትቀ ፫
መጥ ለምኜህ ነበር ሌላ ትምህርት እንዳያመጡ ትገ
ሥፃቸው ዘንድ። ግብ፡ ሐዋ፡ ፳ ፩።
ተረትን እንዳያመጡ ሰውን በሚያስቱ ገንዘብ ፈጥ ፬
ረው የሚናገሩትን ዋዛ ፈዛዛ እንዳያመጡ ክርክርን
ያመጣሉ የታመነውን የእግዚአብሔርን ሕግ ትተው
ጸብ ክርክርን እንዳያመጡ። ምዕ፡ ፬ ፯።
የትእዛዝስ ፍጻሜው በንጹሕ ልብ፡ በበጎ ምግባር፡ ፭
ጥርጥር በሌለበት ሃይማኖት ሆኖ መዋደድ ነው።
ሮሜ ፲፪ ፱-፲።
ከዚህ ወጥተው ወደ ከንቱ ነገር የተመለሱ አሉና። ፮
ምዕ፡ ፮ ፬-፳።
መምህራን ሊሆኑ ሲወዱም ራሳቸው የሚናገሩትን ፯
አያውቁም። ዮሐ፡ ፫ ፲። ምዕ፡ ፮ ፬፡ ፳።
ኦሪት በሕጉ ፀንቶ ለሚፈጽመው መልካም እንደሆነ ፰
እናውቃለን። ሮሜ ፯ ፲፪።
ይህንንም እናውቃለን ሕግ የሚሠራው ለጻድቃን ፱
እንዳይደለ ለኃጢአተኞች ለከዳተኞች ኃጢአትን
ለሚያዘወትሩ ከጽድቅ ለወጡ ሐሳባቸው ለረከሰ፡
አባቶቻቸውን እናቶቻቸውን ዘመዶቻቸውን ለማ
ይረዱ ለነፍሰ ገዳዮች ነው እንጂ። ገላ፡ ፫ ፲፱።
ለአመንዝሮች ወደ ጐልማሳ ሚስት ለሚሄዱ ሰውን ፲
እያፈኑ ለሚሸጡ፡ ለሐሰተኞች፡ በሐሰት ለሚምሉ
ነው እንጂ። ዘፀአ፡ ፳፩ ፲፮። ምዕ፡ ፮ ፰።
እኔ ያመንኩበት ንኡድ ክቡር የሚሆን እግዚአ ፲፩
ብሔር የጌትነቱ ወንጌል የምትናገረውን የሕይወት
ትምህርት በሚቃወሙ ሰዎች ላይ የተሠራም ሕግ
አለ። ምዕ፡ ፮ ፲፭።
የተማመነኝ በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስም ያፀ ፲፪
ናኝ እግዚአብሔርን አመሰግነዋለሁ፡ ለመልእክቱ
ታማኝ አድርጎኛልና። ግ፡ ሐ፡ ፱ ፲፭። ገላ፡ ፩ ፲፫።
እኔ ቀድሞ እሱን የምሰድብ ያመኑበትን የማሳድድ ፲፫

ተማሀለኒ እስመ በኢያእምሮ ገበርኩ በኢአሚን ።
፲፬ ወፈድፈደ ጸጋሁ ለእግዚአብሔር በላዕሌየ ፡ ወሃይማ
ኖቱ ወፍቅሩ ለኢየሱስ ክርስቶስ እግዚእነ ።
፲፭ እሙን ነገሩ ወርቱዕ ይትወከፍዎ በኵሉ እስመ ኢየ
ሱስ ክርስቶስ መጽአ ውስተ ዓለም ከመ ያድኅኖሙ
ለኃጥአን ዘአነ ቀዳሚሆሙ ።
፲፮ ወበሕቱ ተማህለኒ ከመ ያርኢ ትእምርቲሁ በላዕሌየ
ኢየሱስ ክርስቶስ ወብዙኀ ትዕግሥቱ ወእኩኖሙ
አርአያ ለእለ የአምኑ ቦቱ ለሕይወት ዘለዓለም ።
፲፯ ንጉሥ ዘለዓለም ዘኢይመውት ወኢያስተርኢ አም
ላክ ባሕቲቱ ፡ ዘሎቱ ክብር ወስብሐት ለዓለመ ዓለም
አሜን ።
፲፰ ዘንተ ትእዛዘ አማኅፀንኩከ ወልድየ ጢሞቴዎስ ፡
በከመ ተነብዮ ዘላዕሌከ ከመ ትዕናዕ በኵሉ ገድል
ሠናይ ።
፲፱ እንዘ ብከ ሃይማኖት ወሠናይ ግእዝ ፡ እስመ ሀለዉ
እለ አውከኩ እምሃይማኖት ወተሰብሩ ።
፳ እለ ሄሜኔዎስ ወእለ እስክንድሮስ እለ መጠውክ
ዎሙ ለሰይጣን ይትኰነኑ ኢይልመዱ ፀሪፈ ።

## ምዕራፍ ፪ ፤

### ክፍል ፪ ፡ ዘከመ ይደሉ ጸልዮ ለኵሉ ።

፩ አስተበቍዐከ ቀዳሚ ኵሉ ትግበር ጸሎተ ወስኢለ
ወተጋንዮ ።
፪ ወበእንተዝ ጸልዩ ላዕለ ኵሉ ሰብእ ወላዕለ ኵሉ ነገ
ሥት ወመኳንንት ፡ ከመ በህዱእ ወበጽምው ይኩን
ንብረትነ በኵሉ ጽድቅ ወንጽሕ ።
፫ ዝኬ ሠናይ ወኅሩይ በቅድመ እግዚአብሔር መድ
ኃኒነ ።
፬ እስመ ውእቱ ይፈቅድ ኵሉ ሰብእ ይሕየው ወያእ
ምርዋ ለጽድቅ ።
፭ አሐዱ እግዚአብሔር ወአሐዱ ኅሩይ ማእከለ እግዚ
አብሔር ወሰብእ ፡ ኢየሱስ ክርስቶስ ዘኮነ ሰብአ ።
፮ ወመጠወ ርእሶ ቤዛ ኵሉ ወኮነ ሰማዕተ በዕድሚሁ ።
፯ ዘሎቱ ተሠየምኩ ሐዋርያ ወዐዋዴ ፡ እሙነ እብል
ወኢይሔሱ ተሠየምኩ መምህረ ለአሕዛብ በሃይማ
ኖት ወበጽድቅ ።
፰ ወእፈቅድ ለኵሉ ሰብእ ይጸልዩ በኵሉ ገጸ መካን ፡



ሕጉን የምነቅፍ ስሆን ነገር ግን ባለማወቅ ባለማመን
አድርጌዋለሁና ይቅር አለኝ ። ግብ፡ ሐዋ፡ ፳ ፫ ።
የእግዚአብሔር ጸጋው በእኔ ላይ በዛ ፡ የጌታችን የኢ ፲፬
የሱስ ክርስቶስ ፍቅሩና ሃይማኖቱም በኔ ላይ ፀን
ቷልና ይቅር አለኝ ። ሉቃ፡ ፯ ፵፯ ።
ነገሩ የታመነ ነው በሁሉም ሊቀበሉት የሚገባ ነው ፲፭
ኢየሱስ ክርስቶስ እኔ ፊታውራሪያቸው የምሆን ኃጥ
አንን ሊያድናቸው ወደዚህ ዓለም መጥቷልና ።
ማቴ፡ ፲፰ ፲፩ ፡ ሮሜ ፭ ፰ ።
ነገር ግን ኢየሱስ ክርስቶስ ተአምራቱን የትዕግ ፲፮
ሥቱንም ብዛት በኔ ላይ ይገልጽ ዘንድ የዘለዓለም
ድኅነትን ለማግኘት ለሚያምኑበትም አብነት እሆና
ቸው ዘንድ ይቅር አለኝ ።
የዘለዓለም ንጉሥ የማይሞት እሱ ብቻ የማይታይ ፲፯
አምላክ እንደሆነ ለሚያምኑ ለዘለዓለሙ ክብር ምስ
ጋና የሚገባው በእውነት ። መዝ፡ ፲ ፲፯ ፡ ዳን፡ ፯ ፲፬ ።
ልጄ ጢሞቴዎስ ! በንተ እንደተነገረው ትንቢት ፲፰
መጠን ሃይማኖትን ይዘህ በበጎ ገድል ትፀና ዘንድ
ይህን ትእዛዝ አደራ ብየሃለሁ ። ምዕ፡ ፯ ፲፬ ።
ሃይማኖትና መልካም ጠባይ ያለህ ሆነህ ከሃይማኖት ፲፱
ወጥተው ድል የተነሡ አሉና ። ምዕ፡ ፫ ፱ ።
ስድብን እንዳይለምዱ ይቀጡ ዘንድ ለሰይጣን አሳ ፳
ልፌ የሰጠኋቸው እነ ሄሜኔዎስ፡ እነ እለእስክንድ
ሮስ ናቸው ። መዝ፡ ፻፱ ፯ ፡ ፪ ጢሞ፡ ፪ ፲፯ ።

## ምዕራፍ ፪ ።

### ክፍል ፪ ፡ ለሁሉም መጸለይ ስለ ሚገባ ።

ከሁሉ አስቀድሞ ጸሎትን ምልጃን ምስጋናን ታደ ፩
ርግ ዘንድ እማልድሃለሁ ። ፊልጵ ፬ ፮ ።
ስለዚህም ለሰው ሁሉ ጸልዩ ፡ ለነገሥታትና ለመኳን ፪
ንትም ሁሉ ጸልዩ ። ኑሮአችን በጸጥታ በርጋታ
ይሆን ዘንድ ። ኤር ፳፱ ፯ ። ሮሜ ፲፫ ፩ ።
ይህ ነገር በመድኃኒታችን በእግዚአብሔር ዘንድ ፫
ያማረ የተመረጠ ይህ ነው ። ምዕ ፩ ፩ ። ፬ ፲ ።
እሱ ሰው ሁሉ እንዲድንና ሃይማኖትንም እንዲያው ፬
ቃት ይሻልና ። ሕዝ ፲፰ ፳፫ ። ፪ ጴጥ ፫ ፱ ።
እግዚአብሔር አንድ ነው ፡ ሰው ሆኖ በሰውና በእ ፭
ግዚአብሔር መካከል አስታራቂ የሆነው ኢየሱስ
ክርስቶስ አንድ ነው ። ኢሳ ፵፭ ፳፩ - ፳፪ ።
ለሁሉ ቤዛ ራሱን አሳልፎ የሰጠ፡ በጊዜው ጊዜ ፮
መከራን የተቀበለ እርሱ ነው ። ገላ ፩ ፬ ።
እኔ ሐዋርያ አዋጅ ነጋሪ ሁኜ የተሾምኩለት እው ፯
ነቱን እናገራለሁ አልዋሽም ፡ በሃይማኖት በእውነት
ለአሕዛብ መምህር ሆኜ ተሾሚያለሁና ። ግብ ሐዋ
፱ ፲፭ ። ፪ ጢሞ ፩ ፲፩ ።
ሰዎች ሁሉ ያለ መጠራጠር ያለ ማንጐራጐር ፡ እጃ ፰

ወያንሥኡ እደዊሆሙ በንጽሕ እንበለ ነጐርጓር
ወኑፋቄ ።
፱ ወከማሁ አንስትኒ ይትረሰያ ለጸሎት በፈሪሃ እግዚ
አብሔር ወበኀፍረት ወበልቡና ወበአንጽሖ ርእሶን
እምዝሙት ፣ አኮ በሐብላተ ወርቅ ወበባሕርይ ወበአ
ልባስ ቅድው ዘዕፁብ ሤጡ ፣ ወአኮ በተጸፍሮ ሥዕ
ርቶን ።
፲ ዘእንበለ በዘይደልዎን ለአንስት ቀዲሙ አምልኮ
እግዚአብሔር በትምህርተ ጽድቅ ወበምግባረ ሠናይ፤
፲፩ ብእሲትኒ በጽምው ትትመሀር ወትትአዘዝ በኵሉ
የውሃት ።
፲፪ ወብእሲትሰ ትምህር ኢናበውሓ ወኢትመብል ላዕለ
ብእሲ ዳእሙ በጽምው ተሀሉ ።
፲፫ እስመ አዳም ቀደመ ተፈጥሮ ወእምድኅሬሁ ሔዋን።
፲፬ ወአዳምሰ ኢስሕተ አላ ብእሲት ስሕተት ወዐለወት።
፲፭ ወበሕቱ ተሐዩ በእንተ ወሊዳ ለእመ ነበሩ በሃይማ
ኖት ፣ ወበተፋቅሮ ፣ ወበቅድሳት ፣ ወበአንጽሖ ርእ
ሶሙ በአእምሮ ።

ምዕራፍ ፫ ፤

<u>ክፍል ፫ ፣ በእንተ ሢመተ ክህነት ።</u>

፩ አሙን ነገር ዘይፈቅድ ይሠየም ጳጳሰ ሠናየ ግብረ
ፈተወ ።
፪ ወበሕቱ ርቱዕ ይሠየም ጳጳሰ ዘኢያደሉ ለገጽ ዘአ
ልቦ ምክንያት ዘአሐተ ብእሲተ አውሰበ ፣ ብእሲ
ንቁሕ ወጠቢብ ወመፍቀሬ ነግድ ዘአንጽሖ ርእሰ
መምህር ወመገሥፅ ።
፫ ዘኢያበዝኅ ሰትየ ወይን ፣ ዘኢያፈጥን እዴሁ ለዘቢጥ
በቍዕ ዘኢይትገአዝ ዘኢያፈቅር ንዋየ ።
፬ ዘሠናይ ሥርዓተ ቤቱ ፣ ዘበ ውሉድ ዘይትኤዘዙ ፣
በኵሉ ንጽሕ ።
፭ ወዘሰ ኢይክል ሠሪዐ ቤቱ እፎኑ ያስተሐምም ቤተ
እግዚአብሔር ።
፮ ወኢይኩን ዘእምሐዲስ ተክል ከመ ኢይትዐበይ ፣
ወኢይጸለል ወኢይደቅ ውስተ መሥገርተ ሰይጣን።
፯ ወዓዲ ርቱዕ ዘሰብእ አፍአ ይንእድዎ ከመ ኢይደቅ
ውስተ ጽእለት ወመሥገርተ ሰይጣን።
፰ ወዲያቆናትኒ ከማሁ ንጹሐን ወእስትርኩበን እለ
አሐዱ ቃሎሙ ፣ እለ ኢያበዝኑ ሰትየ ወይን እለ
ኢያፈቅሩ ረባኅ ከንቶ ።
፱ እለ የዐቅቡ ምክረ ሃይማኖቶሙ በልብ ንጹሕ ።

ቸውን አንሥተው በአራቱ መዓዝን እንዲጸልዩ እወ
ዳለሁ ። ሚል ፩ ፲፩ ።
እንዲሁም ሴቶች እግዚአብሔርን በመፍራት የሰ ፱
ውን ፊት በማፈር በማስተዋል ራሳቸውን ከዝሙት
በመለየት ለጸሎት ይዘጋጁ ፣ በወርቅ ድሪ ፣ በዕንቍ ፣
ዋጋው ብዙ በሆነ በማረ ልብስ አይደለም ፣ ፀጕ
ራቸውንም በመሠራት አይደለም ። ፩ ጴጥ ፫ ፫ - ፭ ።
ለሴቶች በሚገባቸው እንጂ አስቀድሞ በእውነተ ፲
ኛው ትምህርትና በበጎ ምግባር ፀንቶ እግዚአብሔ
ርን ማምለክ ነው ። ምዕ ፭ ፲ ።
ሴትም በፀጥታ ትማር በፍጹም ቀንነትም ትታዘዝ። ፲፩
ኤፌ ፭ ፳፪ ።
ሴትስ እንድታስተምር አናሰናብታትም በወንድ ላይ ፲፪
አትሠልጥን በዝግታ ትኑር እንጂ ዘፍጥ ፫ ፲፮ ።
አዳም በፊት ተፈጥሮአልና ፣ ከእሱም በኋላ ሔዋን ፲፫
ተፈጥራለችና ። ዘፍጥ ፩ ፳፯ ።
አዳም አልሳተም ፣ ሴት ሳተች በደለች እንጂ ። ዘፍጥ ፲፬
፫ ፮ ። ፪ ቆሮ ፲፩ ፫ ።
ነገር ግን ስለ ልጆቿ ትድናለች ፣ በሃይማኖት ፀፍቅር ፲፭
በንጽሕና ፣ ራሳቸውን በዕውቀት በማንጻት ቢኖሩ ።

ምዕራፍ ፫ ።

<u>ክፍል ፫ ፣ ስለ ክህነት አሿሿም ።</u>

እውነተኛው ነገር ጵጵስና ሊሾም የሚወድ በጎ ነገ ፩
ርን ወደደ ። ግብ ሐዋ ፳ ፳፰ ።
ነገር ግን ፊት አይቶ የማያደላ ሰው ጵጵስና ሊሾም ፪
ይገባል ፤ ምክንያት የሌለበት አንዲት ሴት ያገባ ንቁ
ሰው ብልህ እንግዳ ወዳጅ ራሱን ንጹሕ ያደረገ የሚ
መክር የሚያስተምር ሊሾም ይገባል ። ዘሌ ፳፩ ፲፯ ።
ጠጅ መጠጣትን የማያበዛ ፣ ለመማታት እጁን የማያ ፫
ፈጥን ፣ ምክሩ የሚጠቅም ፣ የማይጣላ ፣ ገንዘብ የማይ
ወድ ሊሾም ይገባል ። ዘሌ ፲ ፰ ። ቲቶ ፩ ፯ ።
የቤቱ ሥርዓት ያማረ ፤ በፍጹም ንጽሕና የሚታዘዙ ፬
ልጆች ያሉት ሊሾም ይገባል ዘዳግ ፳፬ ፲፭ ።
ቤቱን ማስተዳደር የማይችል ሰው የእግዚአብሔርን ፭
ቤት እንደምን ያስተዳድራል ? ።
በድንቁርና ተይዞ እንዳይታበይ ፤ በሰይጣን ወጥመድ ፮
እንዳይያዝ ከአዲስ አማኝ ወገን አይሁን ።
ዳግመኛም የውጪ ሰዎች የሚያመሰግኑት ሊሆን ፯
ይገባል ፣ በስድብ እንዳይወድቅ በሰይጣን ወጥመድ
እንዳይያዝ ። ምዕ ፭ ፲ ። ፩ ቆሮ ፭ ፲፪ - ፲፫ ።
ዲያቆናትም እንዲሁ ንጹሐን የተወሰኑ ፣ ቃላቸው ፰
አንድ የሆነ ፣ ጠጅ መጠጣትን የማያበዙ ፣ ከንቱ ትር
ፍን የማይወዱ ። ፊልጵ ፩ ፩ ። ግብ ፮ ፫ ።
የሃይማኖታቸውን ትምህርት በንጹሕ ልብ የሚጠ ፱
ብቁ ይሁኑ ።

## ኀበ ጢሞቴዎስ ፩ ።

፲ ወሎሙኒ ይቅድሙ አመክሮቶሙ ወእምዝ ይትለ
አኩ እምከመ ኅሩያን እሙንቱ ።
፲፩ ወአንስትኒ ከማሁ እለ አንጽሖ ርእሶን እለ ተምህራ
ሥርዓተ ፡ እለ ኢያስተዳጕጻ ጠባበተ ወርቱዓት ወም
እመናት በኵሉ ይትለአካ ።
፲፪ ወብእሲኒ ዘአሐተ ብእሲተ አውሰበ ዘበ ውሉድ ዘሠ
ናይ ግእዘ ቤቱ ።
፲፫ ወእለሰ ሠናየ ይትለአኩ አንተ ተፀቢ ሚመተ ይግ
በሩ ሎሙ ፡ ወብዙኀ ሞገስ በሃይማኖተ ኢየሱስ ክር
ስቶስ ።
፲፬ ወዘኒ ዘእጽሕፍ ለከ እትአመን ከመ እበጽሐከ ፍጡነ።

፲፭ ወእመሰ ጐንደይኩ ከመ ታእምር ዘከመ ትሠርዕ
ቤተ ክርስቲያኑ ለእግዚአብሔር ሕያው ዐምዳ ወድዳ
ለጽድቅ አማን እስመ ምክሩ ለዝንቱ ጽድቅ ዐቢይ።

፲፮ ዝኬ ዘአስተርአየ በሥጋ ሰብእ ፡ ወጸድቀ በመንፈስ
ወኢስተርአዮሙ ለመላእክት ፡ ወሰበክዎ ውስተ አሕ
ዛብ ፡ ወተአመነ ውስተ ዓለም ፡ ወዐርገ በስብሐት ።

### ምዕራፍ ፬ ፤

### ክፍል ፬ ፡ በእንተ ነባብያነ ሐሰት ።

፩ ወመንፈስ ገሀደ ይነግር ከመ በደኃሪ መዋዕል የዐ
ልዉ ሃይማኖቶሙ ብዙኃን ፡ ወይተልውዎሙ ለአጋ
ንንት እኩያን ወመስሕታን ወትምህርተ ሰይጣን
ዘያናፍቅ ።
፪ ነባብያነ ሐሰት ፡ እለ ንዱዳን በሕሊናሆሙ ።

፫ እለ የሐርሙ አውስቦ፡ ወይከልኡ መባልዕተ ዘእግዚ
አብሔር ፈጠረ ለምእመናን ከመ ይሴሰዩ ወያእኵቱ
እለ የአምርዋ ለጽድቅ ።
፬ እስመ ኵሉ ተግባረ እግዚአብሔር ሠናይ ወአልቦ
ግዱፍ ወኢምንትኒ ለእመ ተወክፍዎ እንዘ የአኵቱ።

፭ እስመ ይትቄደስ በቃለ እግዚአብሔር ወበጸሎት ።
፮ ወዘንተ መሀሮሙ ለአኃዊከ ወትከውን ኅሩየ ላእከ
ኢየሱስ ክርስቶስ ፡ እንዘ ትሴስዮሙ ቃለ ሃይማኖት
ወሠናየ ትምህርተ ዘተምህርከ ።

፯ ለመኃድምተ ዕቤራትሰ ርኩስ እበዮ ፡ ወአግርር ርእ
ሰከ ለጽድቅ ።
፰ እስመ ግረትሰ በሥጋ ለኅዳጥ ዘመን ትበቍዕ ወጽ
ድቅሰ ታሠልጥ በኵሉ ፡ ወባቲ ተስፋ ሕይወት በዝ
ዓለም ወበዘይመጽእ ።
፱ እሙን ነገሩ ወርቱዕ ይትወከፍዎ በኵሉ ።
፲ እስመ በእንተዝ ንሠርሕ ወንጼእል እስመ ተወከልነ

## ወደ ጢሞቴዎስ ፩ ።

እነሱንም አስቀድመው ይፈትኗቸው ከዚህ በኋላ ፲
የበቁ ሆነው ከተገኙ ያገልግሉ ።
ሴቶችም እንዲሁ ሰውነታቸውን የጠበቁ ፡ ሥርዓትን ፲፩
የተማሩ ፡ ሰውን ከሰው የማያጣሉ ብልሆች ቅኖች
በሁሉ የታመኑ ከሆኑ ይላኩ ። ቲቶ ፪ ፫ ።
ወንድም አንዲት ሴት ያገባ ልጆች ያሉት ፡ የቤቱ ፲፪
ሥርዓት ከተከናወነለት ሰው ይሁን ። ቍ ፪ ።
በጎ ማገልገልን ላገለገሉት ከፍተኛውን (ቅስና) ፲፫
ሹመት ይስጧቸው ፡ ኢየሱስ ክርስቶስን በማመን
ብዙ ክብር አለ ። ማቴ ፳፭ ፳፩ ። ፩ ዮሐ ፫ ፳፩ ።
ይህንንም የምጽፍልህ ፈጥኜ እንደምደርስልህ ፲፬
አምኜ ነው ።
የዘገየሁ እንደሆነ ግን ለእውነት ዓምድ መሠረት ፲፭
የሆነው የሕያው እግዚአብሔርን ቤተ ክርስቲያን
እንደምታስተዳድር ታውቅ ዘንድ ነው ፡ የዚህ ጽድቅ
ምሥጢሩ ታላቅ እንደሆነ እውነት ነው ።
ይህም ሰው ሆኖ የታየው መታየት ፡ በመንፈስ የተ ፲፮
ረዳው መረዳት ነው ፡ ለመላእክት የታያቸው ለአሕ
ዛብ ያስተማሩት በዓለም ዘንድ የታመነ ፡ በምስጋና
ያረገው ነው ። ሚክ ፭ ፪ ። ዮሐ ፩ ፲፬ ።

### ም ዕ ራ ፍ ፬ ።

### ክፍል ፬ ፡ ሐሰትን ስለሚናገሩ ።

በኋላ ዘመን ብዙ ሰዎች የሚያስቱትን ክፉዎች አጋ ፩
ንንት የሚያጠራጥረውንም የሰይጣን ትምህርት ተከ
ትለው ሃይማኖታቸውን እንደሚለውጡ ፡ መንፈስ
ቅዱስ በግልጽ ይናገራል ። ዳን ፯ ፳፭ ።
ሐሰትን የሚናገሩ ፡ በአሳባቸው የሚቃጠሉ ። ፪
ጋብቻን እርም ነው የሚሉ ጽድቅን የሚያውቋት በል ፫
ተው ያመሰግኑት ዘንድ እግዚአብሔር ለምእመናን
የፈጠረውን ምግብ የሚከለክሉ ። ዘፍጥ ፱ ፫ ።
እግዚአብሔር የፈጠረው ፍጥረት ሁሉ መልካም ፬
ነውና እያመሰገኑ ቢመገቡት ምንም የሚጣል የለ
በትምና ። ዘፍጥ ፩ ፴፩ ። ግብ ሐዋ ፲ ፲፭ ።
በእግዚአብሔር ቃልና በጸሎት ይከብራልና ። ፭
ለወንድሞችህ ይህን አስተምራቸው ፡ የተማርከውን ፮
በጎ ትምህርትና የሃይማኖትን ነገር ብታስተምራቸው
የኢየሱስ ክርስቶስ ምርጥ አገልጋይ ትሆናለህ ።
ኤር ፲፭ ፲፮ ። ፪ ጢሞ ፩ ፭ ።
የረከሰውን የባልቴት ተረት ግን ተው ራስህን ለጽ ፯
ድቅ አስገዛ ። ፪ ጢሞ ፪ ፲፮ - ፳፫ ፡ ቲቶ ፩ ፲፬ ፡ ፫ ፱።
በሥጋ መገዛት ለጥቂት ዘመን ትጠቅማለች ፡ ጽድቅ ፰
ግን በሁሉም ግዳጅ ትፈጽማለች ፡ በዚህም ዓለም
በሚመጣውም የሕይወት ተስፋ አላት ። መዝ ፴፮ ፬።
ምሳ ፫ ፲፮ - ፲፰ ። ማቴ ፮ ፴፫ ።
ነገሩ እውነት ነው በሁሉም ሊቀበሉት ይገባል ። ፱
ስለዚህ ለሰው ሁሉ ይልቁንም ለምእመናን አዳኝና ፲

በእግዚአብሔር ሕያው ወማሕየዊ ለኵሉ ሰብእ ወፈ
ድፋደሰ ለመሃይምናን ።
፲፩ ከመዝ መሀር ወገሥፅ ።
፲፪ ወአልቦ ዘያስተዓብዳ ለውርዙትከ ወኩኖሙ አርአያ
ወአምሳለ ለመሃይምናን በቃልከ ወበምግባሪከ በፍ
ቅር ወበሃይማኖት ወበንጽሕ ።
፲፫ ወተፀቀብ እስከ እመጽእ በአንብቦ ወበምሂር ፡ ወበገ
ሥፆ ፡ ወበጸልዮ ።
፲፬ ወኢታስትት ጸጋሁ ዘላዕሌከ ዘተውህበከ ምስለ ተነ
ብዮ ወምስለ ሢመተ እደዊሆሙ ለጳጳሳት ።
፲፭ ዘንተ አንብብ ወበዝ ሀሉ ፡ ከመ ይትዓወቅ ሥላጤከ
በኵሉ ።
፲፮ ዑቅ እንከ ርእሰከ በእንተ አንብቦ ፡ ወዘልፈ ሀሉ
ባቲ ፡ ወእመሰ ዘንተ ገበርከ ርእሰከኒ ታድኅን ወዘሂ
ይሰምዐከ።

ሕያው በሆነው በእግዚአብሔር ስም እንደክማለን
እንሰደባለን ። መዝ፡ ፴፮ ፮ ፡ ኤፌ፡ ፩ ፳፫ ።
እንዲህ ምከር አስተምር ። ፲፩
ወጣትነትህን የሚያስንፋት አይኑር በፍቅር በሃይማ ፲፪
ኖት በንጽሕና ፀንተህ በቃልህም በሥራህም ለምእ
መናን ምስሌ አብነት ሁናቸው ። ቲቶ ፪ ፲፭ ።
እስከመጣ ድረስ በማንበብ በማስተማር በመምከር ፲፫
በመጸለይ ፀንተህ ኑር ። ዮሐ፡ ፭ ፴፱ ።
ትንቢት ከመናገርና በጳጳሳት እጅ ከተሾምከው ፲፬
ሹመት ጋር የተሰጠህን በንተ ላይ ያደረገውን የእግ
ዚአብሔርን ጸጋ አታቃልል ። ግብ፡ ሐዋ፡ ፮ ፮ ።
ፍጹምነትህ በሁሉ ይታወቅ ዘንድ ይህን አንብብ ፡ ፲፭
በዚህም ጸንተህ ኑር ።
እንግዲህ መጽሐፍን ስለ ማንበብ ራስህን ዕወቅ ፲፮
ዘወትር በዚያው ፀንተህ ኑር ይህን ብታደርግ ራስህ
ንም የሚሰማህንም ታድናለህ ። ሕዝ፡ ፴፫ ፱ ።

ምዕራፍ ፭ ፤

<u>ክፍል ፭ ፡ በእንተ አክብሮ ልሂቃን ።</u>

፩ ሊቃናተ ኢታመጕጽ ተአዘዝ ከመ ዘለአቡከ ፡ ወለን
ኡሳን ከመ ዘለአኀዊከ ።
፪ ወለልሂቃትኒ ከመ ዘለእምከ ወለንኡሳትኒ ከመ ዘለ
አኀቲከ በኵሉ ንጽሕ ።
፫ ወአክብር ዕቤራተ በጽድቅ ።
፬ ወእመቦ እምኔሆሙ ዕቤር እንተ ባቲ ውሉድ አው
ደቂቀ ውሉድ ይትመሀሩ ቅድመ አሠንዮ ለቤቶሙ፡
ወይሴስዩ አዝማዲሆሙ እስመ ከማሁ ሠናይ ወሥ
ሙር በቅድመ እግዚአብሔር ።
፭ ወእንተሰ ዕቤር በአማን ንጽሕት እንተ ባሕቲታ ትነ
ብር እስመ ትውክልታ እግዚአብሔር ባሕቲቱ ትፀ
መድ ጸሎተ ወትስእል መዓልተ ወሌሊተ ።
፮ ወእንተሰ ትፈግዕ ምስለ ተውኔት ምውት ይእቲ
እንዘ ሕያዋ ።
፯ ወከመዝ ገሥፅ ከመ ኢያድልዉ ወኢያመክንዩ ።
፰ ወዘሰ ኢይሔሊ ለቤቱ ወይገድፍ አዝማዲሁ ወፈድ
ፋደሰ ለእመ ኮኑ እምሰብአ ሃይማኖት ውእቱ ክሕደ
ሃይማኖቶ ወየአኪ እምዘኢየአምን ።
፱ ወለእመ ኀረይከ ዕቤረ ኀረይ እንተ ስሳ ክረምታ
እንተ አሐደ ብእሴ አውሰበት ።
፲ እንተ ይንዕድዋ በኵሉ ምግባረ ሠናይ ፡ ለእመ አል
ኃቀት ውሉዳ ፡ ወለእመ ነግደ ተወክፈት ወለእመ
እግረ ጻድቃን ሐፀበት ፡ ወለእመ ርኁበ አጽገበት ፡
ወኵሎ ምግባረ ሠናይ ለእመ ተለወት ።

ምዕራፍ ፭ ፤

<u>ክፍል ፭ ፡ ሽማግሌዎችን ስለ ማክበር ።</u>

ሽማግሌዎችን አታዋርድ ለአባትህ እንደምትታዘዝ ፩
ታዘዝ እንጂ ለታናናሾችም ለወንድሞችህ እንደም
ትታዘዝ ታዘዝ ። ዘሌዋ፡ ፲፱ ፴፪ ።
ለባልቴቶችም ለእናትህ እንደምትታዘዝ ታዘዝ ለታ ፪
ናናሾችም ለእኅቶችህ እንደምትታዘዝ በፍጹም
ንጽሕና ሆነህ ታዘዝ ። ዮሐ፡ ፲፱ ፳፯ ።
ባልቴቶችን በእውነት አክብር ። ቀ፡ ፭ ። ፫
ከእነሱ ወገን ልጅ ወይም የልጅ ልጅ ያላት ባልቴት ፬
ብትኖር አስቀድሞ ለቤታቸው በጎ ማድረግን ይማሩ
ዘመዶቻቸውንም ይርዱ ፡ እንዲህ ያለው በእግዚአ
ብሔር ፊት ያማረና የተወደደ ነውና ። ማቴ፡ ፲፭ ፬ ።
ብቻዋን የምትኖር በእውነት ንጽሕት የሆነች ባል ፭
ቴት ግን ተስፋዋ እግዚአብሔር ብቻ ነውና ለጸሎት
ጽምድት ትሆናለች ፡ በመዓልትም በሌሊትም ትለ
ምናለች ። ሉቃ፡ ፪ ፴፯ ። ፲፰ ፩ ።
ከዘፈን ከጨዋታ ጋር ተድላ ደስታ የምታደርግ ግን ፮
ሕያው ስትሆን የሞተች ናት ። ሮሜ ፰ ፲፫ ።
እንዲህ ምከር አስተምር ፡ እያመከኙ እንደያደሉ ። ፯
ለቤቱ የማያስብ ዘመዶቹን የሚጥል ይልቁንም ከሃይ ፰
ማኖት ሰዎች ወገን ሲሆኑ እሱ ሃይማኖቱን ክዶአል
ከማያምነውም ይከፋል ። ገላ፡ ፯ ፲ ። ፪ ጢሞ፡ ፫ ፭ ።
ባልቴትን ብትመርጥ ዕድሜዋ ስሳ ዘመን የሆናት ፱
አንድ ባል ያገባች ባልቴት ምረጥ ።
በፍጹም በጎ ምግባር የሚያመሰግኗት ልጆቿን በደ ፲
ንብ ካሳደገች እንግዳን ከተቀበለች ፡ የድኾችን እግር
ካጠበች የተራበውን ካጠገበች በጎ ምግባር ሁሉ ከተ
ከተለች እሷን ምረጥ ። ዘፍ፡ ፲፰ ፬ ፡ ግ፡ ሐ፡ ፲፮ ፲፭ ።

፲፩ ወለንኡሳትሰ መበለታት ተገኃሦን ወኢትሢሞን ከመ ኢይትፈግዓ ላዕለ ክርስቶስ ወይፈቅዳ ይግብኦ ለአውስበ ።
፲፪ ወጽኑሕ ደይኖን ለእመ ክሕዳ ሃይማኖቶን ቀዳሚተ።
፲፫ ወዓዲ አዕርዕተ ወሃኬተ ይትሜሀራ እንዘ የዐውዳ አብያተ ወአኮ አዕርዕተ ባሕቲቶ አላ ዓዲ ከመ ያብዝኃ ነቢበ ወምግባረ ከንቱ ይፈጥራ ነገረ ዘኢሀልው።
፲፬ አፈቅድ እንከ ለንኡሳት ያውስባ ወይትዋለዳ ወይኩና በዓልታተ ቤት ከመ ኢይርከብ ምክንያተ ወኢአሐተኒ በዘይጸብኦን ጸላኢ ከመ ኢያጽእላ ርእሶን ።
፲፭ እስመ ፀ እለ ተመይጡ ወተለውዎ ለሰይጣን ።
፲፮ ለእመበ እምእመናን ዘበ ዕቤር ይዕቀብ፡ ወኢያክብድ ላዕለ ቤተ ክርስቲያን ከመ ትክሀል ለእለ በአማን ዕቤራት ።
፲፯ እላሰ ሠናየ ተልእኩ ቀሲሳን ምክዕቢተ ክብር ይደልዎሙ ወፈድፋደሰ ለእለ ይሠርሑ በቃል ወበምሀሮ፤
፲፰ ወይብል መጽሐፍ ኢትፍጽሞ አፉሁ ለላሕም ሰበ ታከይድ እክለከ ወይደልዎ ዐስቡ ለዘይትቀነይ ።
፲፱ በላዕለ ልሂቅ ኢትስማዕ ውዴተ ዘእንበለ ይዝልፍዎ ክልኤቱ ወሠለስቱ ሰማዕት ።
፳ ወለእለሂ ስሕቱ በቅድመ ኵሉ ገሥፆሙ ከመ ባዕድኒ ይፍራሀ ።
፳፩ አሰምዕ ለከ በቅድመ እግዚአብሔር ወእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወመላእክቲሁ ኅሩያን ከመ ትዕቀብ ዘንተ ትእዛዘ እንዘ ኢታደሉ ወኢታጽድቅ ለሰብእ ቅድመ ፍትሕ ወኢትግበር ምንተሂ በዘትትሔመይ።
፳፪ ወኢትሢም ፍጡነ ወኢመነሂ፡ ወኢትሳተፍ በዝውስተ ኃጢአተ ባዕድ ወአንጽሕ እንከ ርእሰከ ።
፳፫ ወኢትስተይ ማየ ዕራቆ፡ ኅዳጠ ወይነ ቶስሕ በእንተ ሕማመ ከብድከ ወበእንተ ደዌከ ዘዘልፍ ።
፳፬ ፀ ሰብእ ዘይትዐወቆ ኃጢአቱ ወይትበደሮ ውስተ ደይን፡ ወፀ ዘይተልዎ ኃጢአቱ ።
፳፭ ወከማሁ ዘሂ ይገብር ሠናየ ይትዐወቅ፡ ወዘሂ ካልእ ምግባሩ ኢይትከበት ።

ምዕራፍ ፮፤

<u>ክፍል ፮፡ በእንተ ሠሪዐ ቤት ።</u>

፩ ወኵሉ ነባሬ ወቅኑይ እክብሩ አጋእዝቲክሙ በኵሉ ከመ ኢይፅርፉ ላዕለ ስመ እግዚአብሔር ወላዕለ ትምህርቱ ።



ወጣቶቹ ሴቶች ግን ተለያቸው አትሹማቸው ተመልሰው ባል ሊያገቡ ወደው በክርስቶስ ተድላ ደስታ እንደያደርጉበት ። ፲፩
የቀደመችውን ሃይማኖታቸውን ቢክዱ ፍዳቸው ይቈያቸዋል ። ዕብ፡ ፮ ፬ - ፮ ። ፲፪
በዚያውም ላይ ቤት ለቤት እየዞሩ ሥራ ፈትነትንና ስንፍናን ይማራሉ ሥራ መፍታትን ብቻም አይደለም ግን እንደገና ወሬንና ከንቱ ሥራን ሊያበዙ የሌለውን ነገር ፈጥረው ይናገራሉ እንጂ ። ፪ ተሰ፡ ፫ ፲፩። ፲፫
እንግዲህ ወጣት ሴቶች ባል አግብተው ልጅ ወልደው ባለ ንብረት እንዲሆኑ እወዳለሁ ዲያብሎስ ድል የሚነሳቸው ገንዘብ አንዳች ምክንያት እንዳያገኝና ራሳቸውን እንዳያስነቅፉ። ፪ ሳሙ ፲፪ ፲፫፡ ዳን፡ ፮ ፬። ፲፬
ተመልሰው ሰይጣንን የተከተሉ አሉና። ምዕ፡ ፪ ፮ ። ፲፭
ከምእመናን ወገን ባልቴት ያለችው ቢኖር ይርዳት ቤተ ክርስቲያን በእውነት ረዳት የሌላቸውን ባልቴቶች መርዳትን ትችል ዘንድ አያስቸግር ። ፲፮
በሚገባ ያገለገሉ ቄሶች ግን ዕጽፍ ድርብ ክብር ይገባቸዋል ይልቁንም በቃል በማስተማር ሥራ ለሚደክሙት ይገባቸዋል ። ሮሜ ፲፪ ፰ ። ገላ፡ ፮ ፮ ። ፲፯
መጽሐፍ እህልህን በምታበራይበት ጊዜ በሬውን አፉን አትሠረው ለሚሠራ ዋጋው ይገባዋል ይላልና። ዘዳግ፡ ፳፭ ፬ ። ፩ ቆሮ፡ ፱ ፱፡ ሉቃ፡ ፲ ፯ ። ፲፰
ሁለት ወይም ሦስት ምስክሮች ሳይመሰክሩበት በሽማግሌ ላይ ነገር አትስማ ። ዮሐ፡ ፰ ፲፯ ። ፲፱
የተሳሳቱትንም በሰው ሁሉ ፊት ገሥፃቸው ሌላውም ይፈራ ዘንድ ። ዘዳግ፡ ፲፫ ፲፩፡ ኤፌ፡ ፭ ፲፪ ። ፳
በእግዚአብሔርና በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ በኅሩያን መላእክቱ ፊት አዳኝብሃለሁ፡ ሳታደላ ይህን ትእዛዝ ትጠብቅ ዘንድ ከፍርድ አስቀድሞ ሰውን እውነተኛ እንዳትለው በምንም በምን የምትታማበትን አታድርግ ። ፳፩
ማንንም ማን ፈጥነህ አትሹም በዚህ ምክንያት በሌላው ኃጢአት ተባባሪ አትሁን፡ እንግዲህ ራስህን አንጻ ። ግብ፡ ሐዋ፡ ፮ ፮፡ ፪ ዮሐ፡ ፲፩ ። ፳፪
በዶውን ውኃ አትጠጣ ስለ ሆድህ በሽታ ስለ ዘወትር ደዌህ ጥቂት ወይን ጨምር ። መዝ፡ ፻፬ ፲፭ ። ፳፫
በሕይወት ሳለ ኃጢአቱ የሚታወቅበት አለ በሚቀበርበት የሚታወቅበትም ጊዜ አለ፡ ከሞተም በኋላ የሚከተለው አለ ። ፳፬
እንዲሁ በጎ የሚሠራ ይታወቃል፡ ሥራው ሌላ የሆነም አይደበቅም ። ገላ፡ ፭ ፳፪ ። ፳፭

ምዕራፍ ፮ ።

<u>ክፍል ፮፡ ቤተ ሰብን ሠርቶ ቀጥቶ ስለ ማሳደር ።</u>

ቤተ ሲብ አገልጋይም ሁሉ ጌቶቻችሁን በሁሉ አክብሩ የእግዚአብሔርን ስምና ወንጌልን እንዳይነቅፉ ። ኤፌ፡ ፮ ፭ ። ቲቶ ፪ ፱ ። ፩

፪ ወእለሰ ቦሙ አጋእዝት መሃይምናን ኢያስተሐቅሩ
እስመ አኀዊሆሙ እሙንቱ በሃይማኖት ፡ ዓዲ ፈድ
ፋደ ይትቀነዩ ሎሙ እስመ ምእመናን ወፍቁራን
እሙንቱ ፡ ወለእሉ ይትወከፉ ወይትለአኩ በፍሥሐ
ሎሙ ከመዝ መሀር ወገሥፅ ወአስተብቍዖሙ ።

፫ ወእመሰቦ ዘይሜህር ካልአ ወኢይገብእ ኀበ ትም
ህርተ ነገረ ሕይወት ዘውእቱ ቃለ እግዚእነ ኢየሱስ
ክርስቶስ ወኀበ ትምህርተ ጽድቅ ።

፬ ውእቱኬ ዘይትዔበይ እንዘ አልቦ ዘየአምር ዘእንበለ
መቅሠፍተ ዘየኀሥሥ ወነገረ ጋእዝ ፡ ዘእምኔሁ ይመ
ጽእ ተሐምሞ ወተቃንኦ ፀሬፍ ወምክር እኩይ ወአ
ስተዳጕጾ ሰብእ ።

፭ ወእሉ ሙስናን ወውፁዓን እምጽድቅ ወይረስይዎ
ለጽድቀ እግዚአብሔር ተግባረ ተገኀሦሙ ለእሉ ።

፮ እስመ ለነሰ ተግባርነ ዐቢይ ውእቱ ፈሪሀ እግዚአ
ብሔር ።

፯ እስመ አልቦ ዘአምጻእነ ውስተ ዓለም ፡ ወአልቦ ዘን
ክል ነሢአ እምኔሁ ።

፰ ወእምከመ ረከብነ ሲሳየነ ወዐራዘነ የአክለነ ።

፱ ወእለሰ ይፈቅዱ ይብዐሉ ይወድቁ ውስተ መንሱት
ወብዙኅ መሣግረ ፍትወት ዘዐበድ ዘይብእሶሙ ወዘ
ያሰጥሞሙ ለሰብእ ውስተ ተሠርዎ ወሞት ።

፲ እስመ ሥርወ ለኵሉ እኩይ አፍቅሮ ንዋይ ፡ እስመ
ብዙኃን እለ በዘቲ ስሕቱ ወዐለዉ ሃይማኖቶሙ
ወኀሠሡ ለርእሶሙ ብዙኀ መቅሠፍተ ።

፲፩ ወአንተሰ ብእሴ እግዚአብሔር ጕየይ እምዝ ወዴ
ግን ጽድቀ ፡ ወምሂረ ፡ ወሃይማኖተ ፡ ወተፋቅሮ ፡ ወት
ዕግሥተ ወትሕትና ።

፲፪ ተጋደል ሠናየ ገድለ በሃይማኖት ለተመጥዎ ሕይ
ወት ዘለዓለም ዘሎቱ ተጸዋዕከ ወአመንከ ሠናየ
አሚነ በቅድመ ብዙኃን ሰማዕት ።

፲፫ ከመዝ እኤዝዘከ በቅድመ እግዚአብሔር ዘኵሎ
ሙታነ ያሐዩ ወኢየሱስ ክርስቶስ ዘኮነ ሰማዕተ በቅ
ድመ ጲላጦስ ጳንጤናዊ ።

፲፬ በሠናይ አሚን ከመ ትዕቀብ ዘንተ ትእዛዘ በንጽሕ
እንዘ ኢታደሉ እስከ ምጽአቱ ለእግዚእነ ኢየሱስ
ክርስቶስ ።

፲፭ ዘያስተርኢ በዕድሜሁ ዘባሕቲቱ ብፁዕ ወኃያል
ንጉሠ ነገሥት ወእግዚአ አጋእዝት ።

፲፮ ውእቱ ባሕቲቱ ዘኢይመውት ወቦቱ ብርሃን ዘኢይ

ምእመናን ጌቶች ያሏቸውም ቢኖሩ አያቃልሉ እነሱ ፪
በሃይማኖት ወንድሞቻቸው ናቸውና ይልቁንም አብ
ልጠው ያገልግሏቸው ምእመናንና ወዳጆቻቸው ናቸ
ውና ቃላቸውን ተቀብለው ደስ ብሎአቸው እነሱን
ያገልግሉ ፡ እንዲህ ምክር አስተምር ማልዳቸውም ።
ምዕ ፡ ፬ ፲፩ ፡ ቲቶ ፫ ፰ ።
ሌላ የሚያስተምር ሰው ቢኖር ፡ ድኅነት ወደሚገኝ ፫
በት ትምህርት የማይመለስ ይኸውም የጌታችን
የኢየሱስ ክርስቶስ ቃል ነው ፡ ወደ እውነተኛው
ትምህርትም የማይመለስ ቢኖር ። ገላ ፡ ፩ ፮ - ፱ ።
የሚያውቀው ሳይኖር የሚታበይ እሱ ነው መቅሠ ፬
ፍትንና ጸብ ክርክርን ይሻል እንጂ ፡ ምንም ምቀኝነት
መቃናት መሳደብ ክፉ ምክርና ሰውን ከሰው ማጣ
ላት የሚመጣበት ። ፩ ቆሮ ፡ ፰ ፪ ።
እነዚህ ድል የተነሡ ከእውነት የወጡ ናቸው የእግ ፭
ዚአብሔርንም ወንጌል መናገጃ ያደርጉታል እነዚህን
ተለያቸው ። ፪ ጢሞ ፡ ፫ ፰ ።
ለእኛስ ደገኛ ተግባራችን እግዚአብሔርን መፍራት ፮
ነው ። መዝ ፡ ፴፮ ፲፮ ፡ ሉቃ ፡ ፲፪ ፴፩ - ፴፪ ።
ወደ ዓለም ያመጣነው የለንም ፡ ከእሱም የምንወስ ፯
ደው የለምና ። መክ ፡ ፭ ፲፪ ።
ልብሳችንን ምግባችንን ካገኘን ይበቃናል ። ዘፍጥ ፡ ፰
፳፰ ፳ ፡ ምሳ ፡ ፴ ፰ ።
በለጸጋ ሊሆኑ የሚወዱ ግን ወደ ጥፋትና ወደሚገ ፱
ዳቸው ሰዎችንም ከመቅሠፍትና ከሞት ላይ ወደሚ
ጥላቸው ስንፍና ወደሚያመጣው ወደ ብዙ የፈቲው
ወጥመድ ይወድቃሉ ። ምሳ ፡ ፳፫ ፬ ፡ ፳፰ ፳፪ ።
የክፉ ነገር ሁሉ ሥሩ ገንዘብ መውደድ ነውና ፡ ፲
በዚህ የተሳሳቱ ሃይማኖታቸውን የለወጡ በራሳቸው
ብዙ መቅሠፍትን ያመጡ ብዙዎች ናቸውና ። ዘፀ ፡
፳፫ ፰ ፡ ሉቃ ፡ ፲፪ ፲፭ - ፳፩ ።
የእግዚአብሔር ሰው አንተ ግን ! ከዚህ ርቀህ ጽድ ፲፩
ቅን ፡ ማስተማርን ፡ ሃይማኖትን ፡ ፍቅርን ፡ ትዕግሥትን ፡
ትሕትናን ተከተል ። ፪ ጢሞ ፡ ፪ ፳፪ ፡ ዕብ ፡ ፲፪ ፲፬ ።
በብዙ ምስክሮች ፊት በጎ እምነትን ያመንክበትን ፲፪
የተጠራህለትን ዘለዓለማዊ ሕይወትን ለማግኘት
በሃይማኖት ፀንተህ በጎ ገድልን ተጋደል ። ዘኁ ፡ ፲ ፭ ።
ሙታንን ሁሉ በሚያስነሣቸው በእግዚአብሔር ፊት ፲፫
በጳንጦሱ ሰው በጲላጦስ ፊት በመሰከረ በኢየሱስ
ክርስቶስም ፊት እንዲህ አዝዛለሁ ። ዘዳ ፡ ፴፪ ፴፱ ።
ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ እስከሚመጣበት ቀን ድ ፲፬
ረስ በበጎ እምነት ፀንተህ ሳታደላ በንጽሕና ይህን
ትእዛዝ ትጠብቅ ዘንድ ። ፩ ተሰ ፡ ፫ ፲፫ ።
በጊዜው ጊዜ የሚገለጥ ኃደኛ እሱ ብቻ ንኡድ ፲፭
ክቡር የሚሆን ፡ ኃያል የነገሥታት ንጉሥ ፡ የጌቶች
ጌታ እሱ ነው ። ዘዳግ ፡ ፲ ፲፯ ፡ ራእ ፡ ፲ ፡ ፲፯ ፲፬ ።
እሱ ብቻ የማይሞት የማይሻር ብርሃን ገንዘቡ የሚ ፲፮

ጠፍአ እምቅድመ ዓለም ዘአልቦ ዘርእዮ ሰብእ፡ ወአልቦ ዘይክል ርእዮቶ ዘሎቱ ክብር ወስብሐት ወኃይል ለዓለመ ዓለም አሜን ።

፲፯ ለአብዕልተ ዝንቱኒ ዓለም አዝዞሙ ከመ ኢይትዐበዩ፡ ወኢይትአመንዎ ለብዕሎሙ ኃላፊ ዘእንበለ በእግዚአብሔር ሕያው፡ ዘውእቱ ይሁበነ በብዝኀ ብዕሉ ኵሎ ከመ ንትፈሣሕ ።
፲፰ ከመ ይግበሩ ግብረ ሠናየ ወይብዐሉ በገቢረ ጽድቅ ወይኩኑ ራትዓነ ወጸጋውያነ ወሱቱፋነ ።

፲፱ ወይሣርሩ ለርእሶሙ መሠረተ ሠናየ ለዘይመጽእ ዓለም ከመ ይርከቡ ሕይወተ ዘበአማን ።

፳ ኦ ጢሞቴዎስ ዕቀብ ማኅፀንተከ ተገኀሥሙ ለርኩሳን እለ ያመጽኡ ነገረ ከንቶ ወያሴስልዋ ለጽድቅ በሐሰት ።
፳፩ እስመ እሉ ስሕቱ እምተስፋ ሃይማኖት፡ ጸጋ ምስሌከ አሜን ።

ተፈጸመት መልእክተ ቀዳማዊት ኀበ ጢሞቴዎስ ወተጽሕፈት በአቴና ወተፈነወት በእደ ቲቶ ።
ወስብሐት ለእግዚአብሔር፡ አሜን ።



ሆን ዓለም ሳይፈጠር የነበረ ያየው ሰው የሌለ ሊያየውም የሚችል የሌለ ክብር ምስጋና ከሀሊነት ገንዘቡ የሚሆን እሱ ለዘለዓለሙ፡ አሜን በእውነት ።
ዮሐ፡ ፩ ፲፰፡ ፪ ዜና መዋ፡ ፳ ፲፩ ።
የዚህን ዓለም ባለጠጎችም ደስ ይለን ዘንድ በባለጸግነቱ ብዛት ሁሉን በሚሰጠን በሕያው እግዚአብሔር እንጂ በኃላፊው ሀብታቸው እንዳይታመኑና እንዳይታበዩ እዘዛቸው ። መዝ፡ ፷፪ ፲፩ ። ፲፯
በጎ ሥራ እንዲሠሩ የእውነትን ሥራ በመሥራት እንዲከብሩ ቅኖች ለጋሶች ተባባሪዎች እንዲሆኑ እዘዛቸው ። ፲፰
እውነተኛውን ሕይወት ያገኙ ዘንድ ለሚመጣው ዓለም ለራሳቸው በጎ ቢጋርን ይበግሩ ዘንድ እዘዛቸው ። ማቴ፡ ፮ ፳ ። ፲፱
ጢሞቴዎስ ሆይ ! አደራህን ጠብቅ ከንቱ ነገር የሚያመጡትን ዕውነትን ድል የተነሡትን በሐሰት የሚለውጡትን ተለያቸው ። ፪ ጢሞ፡ ፩ ፲፪ ። ፳
እነሱ በሃይማኖት ከሚገኘው ተስፋ ወጥተዋልና ጸጋ ከንተ ጋር ይሁን፡ አሜን ። ፪ ጢሞ፡ ፪ ፲፰። ፳፩

በአቴና ተጽፋ በቲቶ እጅ ወደ ጢሞቴዎስ የተላከች መጀመሪያዪቱ መልእክት ተፈጸመች ።
ለእግዚአብሔር ምስጋና ይሁን፡ አሜን ።

# ኀበ ጢሞቴዎስ ፪ ።

## ምዕራፍ ፩ ።

### ክፍል ፩፡ በእንተ ተዘክሮ እኍ ።

፩ እምጳውሎስ ሐዋርያሁ ለኢየሱስ ክርስቶስ በፈቃደ
እግዚአብሔር ወበተስፋ ሕይወት እንተ በኢየሱስ
ክርስቶስ ።
፪ ለጢሞቴዎስ ወልድየ ዘአፈቅር ሰላም ለከ ወሣህል
ወጸጋ እግዚአብሔር አቡነ ወእግዚእነ ኢየሱስ
ክርስቶስ ።
፫ አአኵቶ ለእግዚአብሔር ዘኪያሁ አመልክ በልብ
ንጹሕ እምፍጥረትየ፡ ወዘልፈ እዜክረከ በጸሎትየ
መዓልተ ወሌሊተ ።

፬ ወእፈቱ እርአይከ ወእዜክር አንብዐከ ።
፭ ወእትፌሣሕ ተዘኪርየ ሃይማኖተከ ዘአልቦ ኑፋቄ
እንተ ኀደረት ላዕለ እምከ ኤውንቄ ወእምሔውትከ
ሎይድ ወእፌጽም ፍሥሐየ ወእትአመን ከመ
ላዕሌከኒ ።
፮ ወበእንተዝ እዜክረከ ከመ ይትሐደስ ጸጋሁ ለእግዚ
አብሔር ዘረከብከ በሢመተ እዴየ ላዕሌከ ።

፯ እስመ አከ መንፈሰ ፍርሀት ዘወሀበነ እግዚአብሔር
ዘእንበለ መንፈሰ ኃይል ወንጽሕ ወተፋቅሮ ወጥበብ።

፰ ወኢትኅፈር እንከ በእንተ ስምዐ ለእግዚእነ ወኢ
ታስተኀፍረኒ ኪያየ ሙቁሐ ዳእሙ ፃሙ ለምህሮ
በኃይለ እግዚአብሔር ዘአድኃነነ ወጸውዓነ በጽዋ
ዔሁ ቅዱስ ።
፱ ወአኮ በከመ ምግባሪነ ዳእሙ በከመ ፈቃዱ ወጸ
ጋሁ ዘተውህበ ለነ በኢየሱስ ክርስቶስ እምቅድመ
ዓለም ።
፲ ወአስተርአየ ይእዜ በምጽአቱ ለእግዚእነ ኢየሱስ
ክርስቶስ መድኃኒነ ዘሰዐሮ ለሞት ወአብርሃ ለሕይ
ወት ወአሰሰለ ሙስና በትምህርተ ወንጌሉ ።
፲፩ ዘሎቱ ተሠየምኩ ሐዋርያ ወዐዋዴ ወመምህረ ለአ
ሕዛብ ።
፲፪ ወበእንቲአሁ አሐምም ወኢይትኄፈር እምዘ አነ
በቱ እስመ አአምር ዘተአመንኩ ወእትአመንኒ ከመ
ይክል ዐቂበ ሊተ ዘአማኅፀነኒ እስከ ይእቲ ዕለት ።

፲፫ ወይኩን ለከ አርአያ ውእቱ ቃለ ሕይወት ዘሰማዕከ
በኀቤየ በሃይማኖት ወበፍቅረ ኢየሱስ ክርስቶስ ።
፲፬ ዕቀብ ማኅፀንተከ ሠናየ በመንፈስ ቅዱስ ዘኀዱር
ላዕሌከ ።

# ወደ ጢሞቴዎስ ፪ ።

## ምዕራፍ ፩ ።

### ክፍል ፩፡ ወንድምን ስለ ማስታወስ ።

በእግዚአብሔር ፈቃድ በኢየሱስ ክርስቶስ በምትገ ፩
ኘው በሕይወት አለኝታ የኢየሱስ ክርስቶስ ሐዋርያ
ከሆነው ከጳውሎስ ። ዮሐ፡ ፩ ፬ ፤ ፩ ዮሐ፡ ፲፩ ፲፫ ።
ለምወድህ ልጄ ለጢሞቴዎስ ! ትድረስ ሰላም ለአንተ ፪
ይሁን ያባታችን የእግዚአብሔር ይቅርታ የጌታችን
የኢየሱስ ክርስቶስ ጸጋ ይደረግልህ ። ፩ ጢሞ፡ ፩ ፪።
ከተወለድኩ ጀምሮ በንጹሕ ልብ እሱን የማመል ፫
ከው እግዚአብሔርን አመሰግነዋለሁ በቀንም በሌሊ
ትም በምጸልየው ጸሎት ዘወትር አስብሀለሁ። ግ፡ ሐ፡
፳፫ ፩ ፤ ፳፬ - ፲፮ ፤ ሮሜ ፩ ፰ - ፱ ።
ዕንባህን አስቤ ላይህ እወዳለሁ ። ፬
በእናትህ በኤውንቄና በአያትህ በሎይድ ላይ ያደረ ፭
ችውን ጥርጥር የሌለበት ሃይማኖትህን አስቤ ደስ
ይለኛል፡ባንተም ፀንታ እንዳለች ተማምኜ ደስታዬን
እፈጽማለሁ ። ግብ፡ ሐዋ፡ ፲፮ ፩ ።
ስለዚህም በአንብሮተ እድ በሾምኩህ ሹመት ምክን ፮
ያት ያገኘኸው የእግዚአብሔር ጸጋ ይታደስ ዘንድ
አስብሀለሁ ። ፩ ተሰ፡ ፫ ፲፱ ፤ ፩ ጢሞ፡ ፬ ፲፬ ።
እግዚአብሔር የመፍራትን መንፈስ የሰጠን አይደ ፯
ለምና የኃይል የንጽሕና የፍቅር የጥበብ ነው እንጂ።
ሚክ፡ ፫ ፰ ፤ ሉቃ፡ ፳፬ ፵፱ ፤ ሮሜ ፰ ፲፭ ።
እንግዲህ ለጌታችን ስለ መመስከር አትፈር የታሠር ፰
ኩለትን እኔንም አታሳፍረኝ በዳነንና በልዩ አጠራር
በጠራን በእግዚአብሔር ኃይል ለማስተማር ድከም
እንጂ ። ሮሜ ፩ ፲፮ ።
የጠራንም እንደ ሥራችን አይደለም፡ ዓለም ሳይፈ ፱
ጠር በኢየሱስ ክርስቶስ እንደ ተሰጠን እንደ ቸር
ነቱና እንደ ፈቃዱ ነው እንጂ ።
ሞትን በሻረው ሕይወትን በገለጣት በወንጌል ትም ፲
ህርት ጥፋትን በአራቀ በኢየሱስ ክርስቶስ መምጣት
ዛሬ የተገለጠ ። ሮሜ ፲፮ ፳፭ ፤ ፪ ቆሮ፡ ፲፭ ፶፭ ።
ለአሕዛብ መምህር ያዋጅ ነጋሪ ሐዋርያ ሆኜ የተሾ ፲፩
ምኩለት ። ፩ ጢሞ፡ ፪ ፯ ።
ስለ እርሱ መከራዬም እቀበልለት ካለሁበት መከራ ፲፪
የተነሣ አላፍርም ያመንኩትን ዐውቃለሁና እስከዚ
ያችም ቀን ድረስ ያስጠበቀኝም ሊጠብቅልኝ እንደ
ሚችል አምናለሁና ። ምዕ፡ ፬ ፰ ።
በኢየሱስ ክርስቶስ ፍቅርና በሃይማኖት ፀንተህ ከእኔ ፲፫
ዘንድ የሰማኸው ያየሕይወት ቃል አብነት ይሁንህ ።
ባንተ ላይ በደረው በመንፈስ ቅዱስ በጎ አደራህን ፲፬
ጠብቅ ። ፩ ጢሞ፡ ፮ ፳ ።

፲፭ ወዘንተኒ ተአምር ከመ ዐለዉኒ ኵሎሙ እለ በእስያ
እለ ፊሎጎስ ወኤርዋጌኔስ ።
፲፮ ወየሀበ እግዚአብሔር ሣህለ ለቤተ ሄኔሴፎሩ እስመ
ብዙኀ አዕረፈኒ ወኢኀፈረ በእንተ መዋቅሕትየ ።
፲፯ ወበጺሖ ኀበ ሮሜ ፍጡነ ኀሠሠኒ ወረከበኒ ሙቁ
ሕየ ።
፲፰ የሀበ እግዚአብሔር ይርከብ ሣህለ በኀበ እግዚእነ
በይእቲ ዕለት፡ ወመጠነ ተልእከኒ ሠናየ በኤፌሶን
ለሊከ ተአምር ።

ምዕራፍ ፪ ።

ክፍል ፩፡ በእንተ ተወክፎተ ገድል ።

፩ ወአንተኒ ወልድየ ዕናዕ በጸጋሁ ለእግዚእነ ኢየ
ሱስ ክርስቶስ ።
፪ ወዘሰማዕከ በላዕሌየ በኀበ ብዙኃን ሰማዕት ኪያሁ
መሀሮሙ ለመሃይምናን ሰብእ እለ ይደልዎሙ ከመ
ይምሀሩ ለባዕዳን ።
፫ ወፃሙ ከመ ኄር መስተጋድል ላእከ ኢየሱስ ክርስ
ቶስ ።
፬ እስመ አልቦ ዘይትቃተል ወይሔሊ ንብረተ ዝ ዓለም
ዘእንበለ ከመ ያድሉ ለዘሜሞ ።
፭ መስተጋድልኒ ኢይከውኖ ምዝጋና ለእመ በሕጉ
ኢተጋደለ ።
፮ ወዘኒ ይፃሙ ሐረሳዊ ግብረ ይቀድም ረኪበ ፍሬሁ ።

፯ ወለቡ ዘእቤለከ የሀብከ እግዚአብሔር ጥበበ በኵሉ።

፰ ተዘከሮ ለኢየሱስ ክርስቶስ ዘተንሥአ እምውታን
እምዘርአ ዳዊት ዘመሀርኩ በስሙ ።

፱ ዘበእንቲአሁ እሠርሕ ወእትሞቃሕ ከመ ጊሒልያ
ወበሕቱ ቃለ እግዚአብሔርሰ ኢይትአሰር ።
፲ በእንተዝ እትዔገሥ በኵሉ በእንተ ኅሩያኒሁ ከመ
እሙንቱሂ ይርከቡ ሕይወተ ዘበኢየሱስ ክርስቶስ
ወስብሐተ ዘለዓለም ዘበሰማያት ።
፲፩ እሙን ነገር እምከመ ዐረይነ መዊተ ንሔሪ ሕይወተ።

፲፪ ወእምከመ ዐረይነ ትዕግሥተ ንሔሪ ነጊሠ፡ ወእመሰ
ክሕድናሁ ውእቱኒ ይክሕደነ ።
፲፫ ወእመኒ ኢአመንናሁ ውእቱሰ ምእመነ ይነብር፡
ወኢይክል ክሒደ ርእሶ ።

ክፍል ፪፡ በእንተ እምነተ ገባሬ ።

፲፬ ከመዝ ዘክሮሙ ወአስምዕ ቅድመ እግዚአብሔር
ኢትትላከዩ በግብር ዘኢይበቊዕ በዘይትገፈትዑ
እለ ይሰምዑ ።



በእስያ ያሉም ሁሉ እነ ፊሎጎስ እነ ኤርዋጌኔስ እንደ ፲፭
ከዱኝ ይህን ታውቃለህ ።
ለሄኔሴፎሩ ወገን ግን እግዚአብሔር ይቅርታውን ፲፮
ይስጠው፡ ስለ መታሠሬ ሳያፍር ብዙ አሳርፎኛልና።
ወደ ሮሜ በደረሰም ጊዜ ፈጥኖ ፈልጎኝ ታስሬ አገ ፲፯
ኘኝ ። ግብ፡ ሐዋ፡ ፳፰ ፲፯ ።
እግዚአብሔር በዚያች ቀን በጌታችን ፊት ይቅርታን ፲፰
ያገኝ ዘንድ ማግኘቱን፡ ይስጠው በኤፌሶንም በጎ
አገልግሎትን እንዳገለገለኝ አንተ ታውቃለህ ።
ማቴ፡ ፳፭ ፴፬፤ ፪ ተሰ፡ ፩ ፲፤ ዕብ፡ ፮ ፲ ።

ምዕራፍ ፪ ።

ክፍል ፩፡ መከራ መቀበል ስለ ሚገባ ።

ልጄ! አንተም በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ጸጋ ፩
ዕና ። መዝ፡ ፳፰ ፭ ።
በብዙ ምስክሮች ፊት ከእኔ የሰማኸውን ትምህርት ፪
ለሌሎች ሊያስተምሩ ለሚገባቸው ለታመኑ ሰዎች
እሱን አስተምራቸው ። ፩ ጢሞ፡ ፫ ፪ ።
የኢየሱስ ክርስቶስ አገልጋይ እንደ መሆንህ እንደ ፫
በጎ አርበኛ ፃር ድከም ። ምዕ፡ ፩ ፰፤ ፬፡ ፭ ።
የሾመውን ደስ ለማሰኘት እንጂ የዚህን ዓለም ኑሮ ፬
እያሰበ ወደ ሰልፍ የሚገባ የለምና ። ፩ ቆሮ፡ ፱ ፳፭ ።
አርበኛም በሚገባ ካልተዋጋ ምስጋና አይገባውም ። ፭

የሚደክም ገበሬ በሥራ አስቀድሞ ፍሬውን ለማግ ፮
ኘት አስቀድሞ ይደክማል ።
የምነግርህን አስተውል እግዚአብሔር በሁሉ ጥበ ፯
ቡን ይስጥህ ።
በስሙ ያስተማርኩለት ከዳዊት ወገን የሆነው ከሙ ፰
ታን ተለይቶ የተነሣው ኢየሱስ ክርስቶስን አስበው።
፪ ሳሙ፡ ፯ ፲፪፤ ፩ ቆሮ፡ ፲፭ ፬ - ፳ ።
እንደ ሌባ ስለ እሱ የምደክምለትና የምታሰርለት ፱
የእግዚአብሔር ቃል ግን አይታሰርም። ኤፌ፡ ፫ ፩-፲፫።
ስለዚህም ስለ ኅሩያኖቹ በሁሉ እታገሣለሁ እነሱም ፲
በኢየሱስ ክርስቶስ የሚገኘውን ሕይወትና በሰማይ
ያለውን የዘለዓለም ክብር ያገኙ ዘንድ። ፪ ቆሮ፡ ፮ ፮።
ነገሩ እውነት ነው በሞት ከተካከልን በሕይወትም ፲፩
እንተካከላለን ። ፪ ቆሮ፡ ፬ ፲፩፤ ፩ ጴጥ፡ ፬ ፲፫ ።
በትዕግሥትም ከተካከልን በመንግሥትም እንተካከ ፲፪
ላለን፡ ብንክደው ግን እሱም ይክደናል ። ማቴ፡ ፲ ፴፫።
ባናምነውም እሱ ግን የታመነ ሆኖ ይኖራል ራሱን ፲፫
አይክድም ። ዘኍል፡ ፳፫ ፲፱፤ ሮሜ ፫ ፫ ።

ክፍል ፪፡ ስለ ገበሬ እምነት ።

እንዲህ ምክራቸው አስተምራቸው በእግዚአብሔር ፲፬
ፊት አዳኝበቸው የሚሰሙ ሰዎች እንዳይሸሹ በማይ
ጠቅም ነገር አትከራከር ። ፩ ጢሞ፡ ፮ ፬ ።

፲፭ አስተፋጥን ከመ ትረሲ ርእሰከ ኅሩየ ለኀበ እግዚአብሔር ከመ ገባሬ ዘኢይትኀፈር ዘርቱዐ ይመትር ቃለ እግዚአብሔር በጽድቅ ።

፲፮ ወለነገረ ርኩሳንሰ ዘአልቦ በቍዕ እበዮ እስመ ያአብይዋ ለኃጢአቶሙ ።

፲፯ ወነገሮሙሂ ከንቱ ከመ ዘይትረአይ ወይልሕቅ በብዙኃን እለ ሄሜኔዎስ ወፊሎጦስ ።

፲፰ እለ አውከኩ እምጽድቅ ወይብሉ ወድአ ከነ ትንሣኤ ምውታን፡ ወይገፈትዑ ሃይማኖቶሙ ለብዙኃን ።

፲፱ ወዘሰ ፅኑዕ በመሠረተ እግዚአብሔር ይቀውም እንዘቦ ዝንቱ ማዕተብ ወየአምሮሙ እግዚአብሔር ለእሊኣሁ ወይርሐቅ እምዐመፃ ኵሉ ዘይሰሚ ስመ እግዚአብሔር ።

፳ ውስተ ቤትኒ ዐቢይ አኮ ባሕቲቱ ንዋየ ወርቅ ወብሩር ዓዲቦ ዘዕፅኒ ወዘልሕኵትኒ ቦ ዘለክብርኒ ወቦ ዘለኀሣርኒ ።

፳፩ ወእመቦ ዘአንጽሐ ርእሶ እምዝ እኩይ ይከውን ንዋየ ክብር ቅዱስ ወበቍዐ ለመልእክተ እግዚአ ወድልወ ለኵሉ ምግባረ ሠናይ ።

፳፪ ጕየያ ለፍትወተ ውርዙት ወዴግና ለጽድቅ ወለሃይማኖት፡ ተፋቅሮ ወሰላም ምስለ ኵሎሙ እለ ይጼውዕዎ ለእግዚአብሔር በልብ ንጹሕ ።

፳፫ እበዮ ለነገረ ዕበድ ወሥላቅ ወተኀሥሦ ከንቱ ተአምር ከመ መንሡተ ያመጽእ ።

፳፬ ወገብረ እግዚአብሔርሰ ኢይትገአዝ አላ ከመ ሕፃን የዋህ ይከውን ምስለ ኵሉ ወመምህረ ወመስተዐግሠ እምኵሉ ።

፳፭ ወይጌሥፅ በየውሃት ለእለ ይትቃረኑ እመቦ ከመ የሀቦሙ እግዚአብሔር ይነስሑ ወያእምርዋ ለጽድቅ።

፳፮ ወያንቅሑ ነፍሶሙ እመሥገርተ ሰይጣን እስመ ወድአ አሥገሮሙ ለተሊወ ፈቃዱ ።

ምዕራፍ ፫ ፤

<u>ክፍል ፩፥ በእንተ መፍቀርያነ ርእሶሙ ።</u>

፩ ወዘንተ ባሕቱ ሕእምር ከመ በደኀሪ መዋዕል ይመጽኡ ዓመታት እኩያት ።

፪ ወይከውኑ ሰብእ መፍቀርያነ ርእሶሙ ባሕቲቶሙ ወመፍቀርያነ ፈጊዕ ወንዋይ ነባብያን ዓላውያን ዝኁራን ዕፉራን ዓላውያነ አዝማዲሆሙ እለ አልቦሙ አኰቴት ውፁዓን እምጽድቅ ።

በእግዚአብሔር ዘንድ ራስህን የተመረጠ ታደርግ ዘንድ ለማስተማር ቸኩል በእውነት የእግዚአብሔርን ቃል በቀጥታ የሚያስተምር ሰው እንደማያፍር ገበሬ ነው ። ፩ ጢሞ፡ ፬ ፯፡ ቲቶ ፪ ፯-፰ ። ፲፭

ነገር ግን ጥቅም የሌለውን የሰነፎችን ነገር ተወው ኃጢአታቸውን ያስፋፏታልና ። ፩ ጢሞ፡ ፬ ፯ ። ፲፮

ከንቱ ነገራቸውም በብዙዎች እንደሚታይና እንደሚሰፋ (ቍስል) ነው እነዚህም ሄሜኔዎስና ፊሎጦስ ናቸው ። ፩ ጢሞ፡ ፩ ፳ ። ፲፯

እሊህ ከጽድቅ የራቁ ትንሣኤ ምውታን ፈጽሞ ተደርጓል እያሉ የብዙዎችን ሃይማኖት የሚለውጡ ናቸው ። ፩ ቆሮ፡ ፲፭ ፲፪ ። ፲፰

እግዚአብሔርን በማመን የፀና ግን ይህ ምልክት ኖሮት ይፀናል እግዚአብሔር ወገኖቹን ይወዳቸዋል የእግዚአብሔርን ስም የሚጠራ ሁሉ ከክፉ ነገር ይርቃል ። ምሳ፡ ፲ ፳፭፡ ማቴ፡ ፯ ፳፫ ። ፲፱

በታላቅ ቤት ውስጥም የወርቅና የብር ዕቃ ብቻ አይኖርም፡ ከዕንጨት ከሸክላ የተሠራም ይኖራል እንጂ፡ ለክብር የሚሆን አለ ለኃሣርም የሚሆን አለ ። ፳

ከዚህ ክፉ ነገር ራሱን ንጹሕ ያደረገ ቢኖር ለጌታው አገልግሎት የሚጠቅም ለበጎም ሥራ ሁሉ የበቃ ልዩ የክብር ዕቃ ይሆናል ። ፳፩

የወጣትነትን ምኞት ትተህ ጽድቅን ሃይማኖትን ተከተላት በንጹሕ ልብ ሆነው እግዚአብሔርን ከሚጠሩት ሁሉ ጋር ፍቅርና ሰላም ይሁንልህ ። ፩ ጢሞ፡ ፮ ፲፩ ። ፳፪

የስንፍናን ነገር መዘባበትን በከንቱ መጠራጠርን ተወው ጥፋትን እንደሚያመጣ ታውቃለህና ። ፩ ጢሞ፡ ፬ ፯ ። ፳፫

የእግዚአብሔር አገልጋይ አይከራከርም ከሁሉ ጋር እንደ ሕፃን የዋህ ይሆናል እንጂ፡ ከሁሉም ታግሦ የሚያስተምር ይሆናል እንጂ ። ቲቶ ፩ ፯ ። ፳፬

የሚቃረኑትን በቅንነት ይመክራል እንጂ ምናልባት እግዚአብሔር ንስሐ ገብተው ጽድቅን እንዲያውቁት ያደርጋቸው እንደሆን ። ፳፭

ከሰይጣን እሸክላም ሰውነታቸውን ይለዩ እንደሆነ ፈቃዱን ለማሠራት ፈጽሞ አጥምዶአቸዋልና ። ፳፮

ምዕራፍ ፫ ።

<u>ክፍል ፩፥ ራሳቸውን ስለሚወዱ ሰዎች ።</u>

ይህን ብቻ ዕወቅ በኋላ ዘመን ክፉ ዘመናት እንደሚመጡ ። ፩ ጢሞ ፬ ፩ ፡ ይሁ ፲፰ ። ፩

ሰዎች ራሳቸውን ብቻ የሚወዱ ተድላ ደስታንና ገንዘብን የሚወዱ ለፍላፊዎች ወንጀለኞች ትዕቢተኞች ተሳዳቢዎች ወላጆቻቸውን የማይረዱ ምስጋና የሌላቸው ከጽድቅ የወጡ ይሆናሉ ። ሮሜ ፩ ፳፱-፴፩ ። ፪

ኀበ ሰብአ ዕብራውያን ።

፫ ነአምር ከመ ተፈጥረ ዓለም በቃለ እግዚአብሔር
ወአስተርአየ ዘኢያስተርኢ ምንትኒ ዘኮነ እምኀበ
ኢሀሎ ።
፬ በተአምኖ ኀየሰ መሥዋዕተ አቤል እምዘ ቃየል
ዘአብአ ለእግዚአብሔር ወበእንቲአሁ ሰማዕተ ኮኖ
ከመ ጻድቅ ውእቱ ወሰማዕቱ እግዚአብሔር በተወ
ክፎ መሥዋዕቱ ፤ ወበእንቲአሁ መዊቶ ዓዲ ተናገረ ።
፭ በተአምኖ ፈለሰ ሄኖክ ከመ ኢይርአዮ ለሞት ወኢ
ተረክበ እስመ ከበቶ እግዚአብሔር ፤ ወዘእንበለ ያፍ
ልሶ ሰማዕተ ኮኖ ከመ አሥመሮ ለእግዚአብሔር ።
፮ ወዘእንበለ ተአምኖሰ ኢይትከሀል ያሥምርዎ ለእግ
ዚአብሔር ፤ ወርቱዕሰ ይትአመን ይቅድም ዘይበ
ውእ ኀበ እግዚአብሔር ወያእምር ከመ ሀሎ ዘይዔ
ሥዮሙ ለእለ የኀሥሥዎ ።
፯ በተአምኖ አመ ነገርዎ ለኖኅ በእንተ ዘኢያስተርኢ
ግብር ዘኀቡእ ፈርሀ ወገብረ ንፍቀ ታቦት በዘያድኅን
ቤቶ እመ ተኮነነ ዓለም ወኮነ ወራሲሃ ለጽድቀ
ሃይማኖት ።
፰ በተአምኖ ሰምዐ ዘተሰምየ አብርሃም ወተአዘዘ
ይሑር ብሔረ ኀበ ሀለዎ ይንሣእ ርስቶ ፤ ወሖረ
እንዘ ኢየአምር ኀበ ይበጽሕ ።
፱ በተአምኖ ፈለሰ ወነበረ ብሔረ ዘአሰፈዎ ከመ ነኪር
በሐይመታት ምስለ ይስሐቅ ወያዕቆብ እለ እሙንቱ
ይወርስዋ ለተስፋሁ ።
፲ እስመ ኮኑ ይጸንሑ ሀገረ እንተ ባቲ መሠረት እንተ
ኬንያሃ ወገባሪሃ እግዚአብሔር ።
፲፩ በተአምኖ ይእቲኒ ሣራ ረከበት ኀይለ ታውዕእ ዘርአ
እንዘ መካን ይእቲ በዘረስአት እስመ ተአመነቶ ከመ
ጻድቅ ዘአሰፈዋ ።
፲፪ እንዘ ክልኤሆሙ ከመ በድን ነፍስቶሙ ከመ ይኩን
ብዝኆሙ ከመ ከከበ ሰማይ ወከመ ኆጻ ባሕር ዘኢ
ይትኌለቍ ።
፲፫ እሉ ኵሎሙ እንዘ ይትአመኑ ሞቱ ወኢረከቡ ተስ
ፋሆሙ ወባሕቱ እምርኁቅሰ ርእይዋ ወተአምኅዋ ፤
ወአእመሩ ከመ ነግድ ወፈላሲ እሙንቱ ዲበ ምድር ።
፲፬ ወእለ ከመዝ ይብሉ በእንቲአሆሙ ያሬእዩ ነገረ
ከመ ሀገሮሙ የኀሥሡ ።
፲፭ ወሶበሰ ይፈቅዱ ሀገረ እንተ እምኔሃ ወፅኡ እምተ
ክህሎሙ ይግብኡ ኀቤሃ ።
፲፮ ወይእዜሰ ተዐውቀ ከመ እንተ ትኄይስ ሀገረ እንተ
በሰማያት ኮኑ ይሴፈዉ ፤ ወበእንተዝ ኢየኀፍር እግ

ወደ ዕብራውያን ሰዎች ።

ዓለም በእግዚአብሔር ቃል እንደ ተፈጠረ ምንም የማ ፫
ይታየው የነበረ የሆነውም ፍጥረት ከለመኖር ወደመ
ኖር መጥቶ እንደታየ እናውቃለን ። መዝ፡ ፴፫ ፮ ።
ቃየል ከቀረበው መሥዋዕት ይልቅ አቤል በሃይማ ፬
ኖት ለእግዚአብሔር ያቀረበው መሥዋዕት ተሻለ ፡
ስለ እሱም ደግ እንደሆነ መሰከረለት ፡ መሥዋዕቱ
ንም በመቀበሉ ምስክሩ እግዚአብሔር ነው ፤ ደግ
እንደሆነም ከሞተ በኋላ ተናገረ ። ዘፍ ፬ ፬ ።
ሄኖክ ሞትን እንዳያየው በሃይማኖት ዐረገ ለሞት ፭
አልተገኘም እግዚአብሔር ሠውሮታልና ሳያሳርገ
ውም እግዚአብሔርን እንዳገለገለው መሰከረለት ።
ያለ ሃይማኖትስ እግዚአብሔርን ማገልገል አይቻልም ፮
ወደ እግዚአብሔር የሚቀርብ ሰው አስቀድሞ ሊያ
ምን ይገባል ለሚሹትም የሚሰጣቸው ዋጋ እንዳለው
ሊያውቅ ይገባዋል ። ኤር፡ ፭ ፫ ፤ ሮሜ ፲፬ ፳፫ ።
ኖኅም ተሠውሮ የማይታየውን ነገር በነገሩት ጊዜ ፯
አምኖ ፈራ ዓለምም በተቀጣ ጊዜ ቤተ ሰቡን ያድን
ዘንድ ክፍል ያላት መርከብ ሠራ አምኖ ለሚገኘ
ውም ጽድቅ ወራሽ ሆነ ። ዘፍጥ፡ ፯ ፰ ።
አብርሃም የተባለው ሰው አምኖ እሺ በጀ አለ ርስ ፰
ቱን ይወርስ ዘንድ ወዳለበት አገርም እንዲሄድ ታዘዘ
ወዴት እንደሚደርስም ሳያውቅ ሄደ ። ዘፍ፡ ፲፪ ፩-፱ ።
በሃይማኖትም ከሀገሩ ወጥቶ ተስፋ በሰጠው ሀገር ፱
ተስፋውን ከሚወርሷት ከይስሐቅና ከያዕቆብ ጋር
እንደ መጻተኛ ሆኖ በድንኳን ኖረ ። ዘፍ ፲፪ ፯ ።
መሠረት ያላትን ሠሪዋ ብልሀተኛዋ እግዚአብሔር ፲
የሆነ ሀገርን ደጅ ይጠኑ ነበርና ። ኢሳ፡ ፴፫ ፳ ።
እሷ ሣራም መካን ሳለች ባረጀችበት ወራት ዘር ታስ ፲፩
ገኝ ዘንድ በሃይማኖት ኃይል አገኘች ተስፋ የሰጣት
እውነተኛ እንደሆነ አምናዋለችና ። ዘፍ፡ ፳፩ ፪ ።
ሁለቱም ሰውነታቸው እንደ በድን ሆኖ ሳለ ብዛታ ፲፪
ቸው እንዳማይቈጠር እንደ ሰማይ ከከብና እንደ ባሕ
ር አሸዋ ይሆን ዘንድ ። ሮሜ ፬ ፲፱ ።
እነዚህ ሁሉ አምነው ሞቱ ተስፋቸውን ግን አላገ ፲፫
ኙም ርቀው አዩዋት እጅ ነሷት እንጂ ፤ በምድር ላይ
እነሱ እንግዳና መጻተኛ እንደሆኑ ዐወቁ ።
እንዲህ የሚሉም አገራቸውን እንደሚሹ ያሳያሉ ፡ ፲፬
የወጡባትንስ ሀገር ቢሹ ኖሮ ወደ እሷ ሊመለሱ ፲፭
በተቻላቸው ነበር ።
አሁን ግን በሰማያት ያለችውን የምትበልጠውን ፲፮
ሀገር ተስፋ ያደርጉ እንደነበር ታወቀ ስለዚህም እግ

ዚአብሔር ከመ ይትበሀል አምላኮሙ እስመ አስተ
ዳለወ ሎሙ ሀገረ እንተ ተሰፈዉ ።
፲፯ በተአምኖ ወሰዶ አብርሃም ለይስሐቅ ወልዱ ከመ
ይሡዖ አመ አመከሮ ።
፲፰ ወአብአ ዘአሐዱ ሎቱ ዘበእንቲአሁ አሰፈዎ ወይ
ቤሎ እምይስሐቅ ይሰመይ ለከ ዘርእ ።
፲፱ ተአሚኖ ከመ ይክል እግዚአብሔር አንሥኦቶ እሙ
ታን፣ ወበእንተዝ ኮነ ሎቱ ተዝካረ ውእቱ ዘተውህበ።
፳ በተአምኖ በዘይከውን ባረኮሙ ይስሐቅ ለያዕቆብ
ወለዔሳው በእንተ ዘሀለዎሙ ይርከቡ ።
፳፩ በተአምኖ አመ ይመውት ያዕቆብ ባረኮሙ ለደቂቀ
ዮሴፍ ለለአሐዱ ወሰገደ ውስተ ከተማ በትሩ ።
፳፪ በተአምኖ አመ ይመውት ዮሴፍ ተዘከረ በእንተ
ፀአቶሙ ለደቂቀ እስራኤል እምድረ ግብጽ ወአዘዘ
በእንተ አዕፅምቲሁ ።
፳፫ በተአምኖ ተወሊዶ ሙሴ ኀብእዎ ሠለስተ አውራኀ
በቤተ አበዊሁ እስመ ርእይዎ ከመ ሠናይ ውእቱ
ሕፃን ወኢፈርሁ ትእዛዘ ንጉሥ ።
፳፬ በተአምኖ ልሂቆ ሙሴ ክሕደ ከመ ኢይበልዎ ወልደ
ወለተ ፈርዖን ።
፳፭ ወአብደረ ይሕምም ምስለ ሕዝበ እግዚአብሔር እም
ይደለው ለሰዓት ወይኩኖ ኃጢአተ ።

፳፮ እስመ አእመረ ከመ የዐቢ ትዕይርተ መስቀሉ ለክር
ስቶስ እምኵሉ መዛግብቲሆሙ ለግብጽ ።
፳፯ በተአምኖ ኀደረ ብሔረ ግብጽ ኢፈሪሆ መዓተ
ንጉሥ እስመ አብደረ ይፍርሆ ለዘኢያስተርኢ እም
ዘይሬኢ ጸኒሖ ዕሜቶ ።
፳፰ በተአምኖ ገብረ ፍሥሐ ወነዘኀ ደመ ከመ ኢያጥ
ፍእ ሎሙ በኵሮሙ ብድብድ ።
፳፱ በተአምኖ ዐደውዋ ለባሕረ ኤርትራ ከመ ዘውስተ
ምድር ይቡስ ወኮነቶሙ መከራ ለግብጽ ተሠጢ
ሞሙ ።
፴ በተአምኖ ወድቀ ዓረፍቲሃ ለኢያሪኮ አመ የዐው
ድዋ ሰቡዐ ዕለተ ።
፴፩ በተአምኖ ረአብኒ ዘማ ኢተሐጕለት ምስለ ዐላው
ያን እስመ ተወክፈቶሙ ለሰብአ ዐይን ወኀብአቶሙ
በሰላም ።
፴፪ ወምንተ እንከ እብል እስመ ኀፀረ ዕለትየ ከመ እዜ
ኑክሙ በእንተ እለ ጌዴዎን፣ ወባርቅ፣ ወዮፍታሔ፣
ወሰምሶን፣ ወዳዊት፣ ወሳሙኤል ወበዕዳንሂ ነቢያት።

፴፫ እለ በተአምኖ ተጋደሉ ወሞፁ ነገሥተ ወአድምዑ
ፍናዊሆሙ፣ ተገብሩ ጽድቀ ወረከቡ ተስፋሆሙ ወፈ
ፀሙ አፈ አናብስት ።

ዚአብሔር አምላካቸው ይባል ዘንድ አያፍርም፣ ተስፋ
ያደረጉትን ሀገር አዘጋጅቶላቸዋልና ።
አብርሃም በተፈታተነውም ጊዜ ልጁ ይስሐቅን ይሠ ፲፯
ዋው ዘንድ በሃይማኖት ወሰደው ። ዘፍ፣ ፳፪ ፪-፲ ።
ስለ እርሱ ከይስሐቅ ዘር ይጠራልሃል ብሎ ተስፋ ፲፰
ያናገረለት አንድ ልጁን ለመሥዋዕትነት አቀረበው ።
እግዚአብሔር ከሙታን እንዲያስነሣለት አምኖ ስለ ፲፱
ዚህ ሰጠው እርሱ መታሰቢያ ሆነለት። ሮሜ ፬ ፲፯።
ይስሐቅ ኋላ ያገኙት ዘንድ ስላላቸው የሚሆነውን ፳
አምኖ ያዕቆብንና ኤሳውን ባረካቸው ። ዘፍ ፳፯ ፳፰።
ያዕቆብም በሚሞትበት ጊዜ የዮሴፍን ልጆች እያን ፳፩
ዳንዱ ባረካቸው በበትሩም ጫፍ ሰገደ፤ ዘፍ፣ ፵፰ ፲፭።
ዮሴፍም በሚሞትበት ጊዜ የእስራኤል ሰዎች ከግ ፳፪
ብጽ የመውጣታቸውን ነገር አሰበ ዐፅሚን ይዛችሁ
ውጡ ብሎ በሃይማኖት አዘዘ ። ዘፍ፣ ፶ ፳፬ - ፳፭ ።
ሙሴ በተወለደ ጊዜ በሃይማኖት ሦስት ወር በአባቱ ፳፫
ቤት ሸሸጉት ፣ ሕፃኑ መልከም እንደሆነ አይተዉታ
ልና የንጉሥንም ትእዛዝ አልፈሩም ። ዘፀ፣ ፩ ፳፪ ።
ሙሴም በሃይማኖት ባደገ ጊዜ የፈርዖን የልጅ ልጅ ፳፬
እንዳይሉት ካደ ። ዘፀ፣ ፲ ፲፪ ።
ላንድ ሰዓት ደስ ብሎት ኃጢአት ከሚሆነው ይልቅ፣ ፳፭
ከእግዚአብሔር ወገኖች ጋር መከራ መቀበልን
ወደደ ።
የክርስቶስ የመስቀሉ ተግዳሮት ከግብጽ ሀብት ሁሉ ፳፮
እንደሚበልጥ አውቆአልና ። ዘፀ፣ ፬ ፳፪ ።
በሃይማኖት የንጉሥን ቍጣ ሳይፈራ ከግብጽ አገር ፳፯
ኖረ ዋጋውን ተስፋ አድርጎ፣ ከሚታየው ይልቅ የማይ
ታየውን ሊፈራ ወዷልና ። ዘፀ፣ ፲ ፲፩ - ፲፰ ።
በሃይማኖት በጉን ሠውቶ ቸነፈር በኵራቸውን እን ፳፰
ዳያጠፋ ደምን ረጨ ። ዘፀአ፣ ፲፪ ፲፪ - ፲፰ ።
በሃይማኖት እንደ ደረቅ ምድር ሆናላቸው የኤርት ፳፱
ራን ባሕር ተሻገሯት ፣ ለግብጻውያን ግን ተስጥመው
ሊቀሩ መከራ ሆነችባቸው ። ዘፀ፣ ፲፬ ፳፪ ።
በሃይማኖት ሰባት ቀን በዞሯት ጊዜ ኢያሪኮ ቅጽ ፴
ርዋ ወደቀ ። ኢያ፣ ፯ ፳ ።
ዘማይቱ ረአብም በሃይማኖት ከከሐዲዎች ጋር አልጠ ፴፩
ፋችም ጕብኞችን ተቀብላ በፍቅር ሠውራቸዋለችና።

እንግዲህ ምን እላለሁ፣ የጌዴዎንን፣ የባርቅን፣ የዮፍታ ፴፪
ሔን፣ የሰምሶንን፣ የዳዊትን፣ የሳሙኤልን፣ የሌሎ
ችንም ነቢያት ነገር ልነግራችሁ ቀን ያጥርብኛልና ።
መሳ፣ ፮ ፲፩ ፤ መሳ፣ ፬ ፮፤ ፲፫ ፳ ።
በሃይማኖት የተጋደሉትን ነገሥታትን ድል የነሡትን ፴፫
ዋጋቸውን ያገኙትን ትሩፋት የሠሩትን ተስፋቸውን
ያገኙትን የአንበሶችን አፍ የዘጉትን። ዳን፣ ፮ ፳፪ ።

፴፬ ወአጥፍኡ ኀይለ እሳት ወድኅኑ እምአፈ ኩናት
ወፀንዑ በሕማሞሙ ወኀየሉ በውስተ ፀብእ ወሰደዱ
ተዓይነ ፀር ።

፴፭ ወነሥአ አንስት ምዉታኒሆን አሕይዎሙ ከመ ዘት
ንሣኤ ወቦ እለ ሞቱ ተኰኒኖሙ እስመ ኢፈቀዱ
ድኅነ ከመ ይርከቡ ሕይወተ እንተ ትኄይስ ።

፴፮ ወቦ እለሂ ቀሠፍዎሙ ወተሣለቁ ላዕሌሆሙ ወሐመ
ይዎሙ ወሞቅሕዎሙ ።
፴፯ ወቦ እለ ወሰርዎሙ በሞሰርት ወወገርዎሙ ወቀተ
ልዎሙ በአፈ መጥባሕት ፡ ወዔሉ በሠቅ ወበሐሜ
ለት ወበዘብድወ ጠሊ ፡ ተጸነሱ ተመንደቡ ሐሙ
ርኅቡ ፀምኡ ።
፴፰ እሉ እሙንቱ ዘኢይደልዎሙ ዓለም ፡ ወዔሉ ውስተ
ገዳም ወውስተ አድባር ወበዓታት ወግበበ ምድር ።
፴፱ ወኵሎሙ ሰማዕተ ኮኑ በሃይማኖት ወኢያድምዑ
ዘአሰፈዎሙ ።
፵ እስመ አቅደመ እግዚአብሔር ርእየ በእንቲአነ እንተ
ትኄይስ ከመ ኢይሠለጡ ዘእንበሌነ ።

ምዕራፍ ፲ወ፪ ፤

## ክፍል ፲ወ፫ ፡ በእንተ ትዕግሥቱ ለክርስቶስ

፩ ወበእንተ ዝንቱ ንሕነኒ እለ ብነ እሙንቱ ሰማዕት
ኵሎሙ ዘየዐውዱነ ከመ ደመና ንግድፍ እምላዕ
ሌነ ኵሎ ክበደ ወሁከተ ኃጢአት ወንሩጽ በትዕግ
ሥት ኀበ ዘጽኑሕ ለነ ተስፋነ ዘሃይማኖት ።
፪ ወንትልዎ ለፍጹም መልአክነ ኢየሱስ ክርስቶስ ዘተ
ዐገሠ ኀፍረተ መስቀል አናኅሲዮ በእንተ ፍሥሓሁ
ዘጽኑሕ ሎቱ ወመነና ለኀፍረት ፡ ወነበረ በየማነ መን
በረ እግዚአብሔር ።
፫ ሐልይዎ እስኩ ለዘከመዝ ተዐገሠ እምኃጥአን ወተ
ናገርዎ በበይናቲክሙ ከመ ኢትሥራሕ ነፍስክሙ
ወኢትድክም ።
፬ እስመ ዓዲክሙ ኢፀናዕክሙ እስከ ለደም ትበጽሑ
ተጋደልዋ ለኃጢአት ወእበይዋ ወአብድርዋ ለትም
ህርተ ተስፋክሙ ።
፭ እስመ ከመ ውሉድ ይብለክሙ ወልድየ ኢታስተጽ
ሕብ ተግሣፀ እግዚአብሔር ወኢትትገኀሥ እምኔሁ
ሶበ ይዘልፈከ አመ ገሠፀከ ።
፮ እስመ ዘአፍቀረ እግዚአብሔር ይጌሥፅ ወይቀሥ
ፍዎ ለኵሉ ውሉድ ዘይትፌቀድ ።
፯ ለተግሣጽክሙ ተዐገሡ እስመ ከመ ውሉዱ ያፈቅረክ
ሙ እግዚአብሔር፡ መኑ ውሉድ ዘኢይጌሥፆ አቡሁ።
፰ ወእመሰ ኢገሠፀክሙ እንደበረ እንትሙ ወኢኮን
ክሙ ውሉደ ወሀረይክሙ ኵልክሙ ።
፱ ወእመሰ አበዊነ እለ ወለዱነ በሥጋ ይጌሥፁነ ወነኀ



ዋዕየ እሳት ያጠፉትን ፡ ከጦር ስለት የዳኑትን ፡ በመ ፴፬
ከራቸው የፀኑትን በሰልፍ ጊዜ የበረቱትን፡ የጠላቶ
ቻቸውን ጭፍራ ያሳደዱትን ነገር እንዳልነግራችሁ
ቀን ያጥረኛል ።
ሴቶችም እንደ ትንሣኤ ቀን ሕያዋን ሁነዉላቸው ፴፭
ሙታኖቻቸውን ወሰዱ፡ ይሙት በቃ ተፈርዶባቸው
የሞቱም አሉ፡ የምትበልጠውን ሕይወት ያገኙ ዘንድ
ከመከራው እንዲድኑ አልወደዱምና ።
የገረፏቸው የዘበቱባቸው አሥረው ያጋዙዋቸውም ፴፮
አሉ ። ኤርም፡ ፳ ፪ ።
በመጋዝ የሰነጠቋቸው በድንጋይ የደበደቧቸው ፴፯
በሰይፍ ስለት የገደሉዋቸው አሉ ፡ ማቅ የተልበ እግር
የፍየል ሌጦ ለብሰው ዞሩ ተጨነቁ ተቸገሩ መከራ
ተቀበሉ ተራቡ ተጠሙ ። ግብ፡ ሐዋ፡ ፯ ፶፱ ።
ዓለም የማይገባቸው እነዚህ ናቸው ፡ ዱር ለዱር ፴፰
ተራራ ለተራራ ዋሻ ለዋሻ ፍርኩታ ለፍርኩታ ዞሩ ።
ሁሉም አምነው መከራ ተቀበሉ ፡ የሰጣቸው ተስፋ ፴፱
ግን አላገኙም ።
እግዚአብሔር ስለኛ አስቀድሞ በይኗልና የምትበ ፵
ልጠውን ያለኛ እንዳይወርሱ ። ምዕ፡ ፲፪ ፳፫ ።

ምዕራፍ ፲፪ ።

## ክፍል ፲፫ ፡ ስለ ክርስቶስ ትዕግሥት።

ስለዚህም እንደ ደመና የሚከቡን እነዚህ ሁሉ ምስ ፩
ክሮች ያሉን እኛ የኃጢአትን ትብትብና ሸክም
አውርደን እንጣል ፡ ሃይማኖት ወደሚያስገኝልን ወደ
ሚጠብቃልን ተስፋችን በትዕግሥት እንገሥግሥ ።
ስለሚጠብቀው ደስታውን ንቆ አቃሎ በመስቀል የደ ፪
ረሰበትን ውርደት የታገሠውን ኀፍረትን የናቃትን
በአብ ዙፋን ቀኝ የተቀመጠው አለቃችን ኢየሱስ
ክርስቶስን እንምሰለው ። ፊልጵ፡ ፪ ፰ ።
እንግዲህ ከኃጥአን መከራ ታግሦ የተቀበለውን እሱ ፫
ን አስቡ፡ አስቡት እርስ በርሳችሁም ተወያዩት ሰውነ
ታችሁም ፈጽማ እንዳትደክም ። ሉቃ፡ ፪ ፴፬ ።
ደማችሁን እስከ ማፍሰስ ለመድረስ ገና አልፀናች ፬
ሁምና ኃጢአትን ተዋጉት እንቢ በሏት ተስፋችሁን
የምታገኙበትን ትምህርት ውደዷት። ምዕ፡ ፲ ፴፫ ።
ልጆቼ እንደ መሆናችሁ ልጄ! የእግዚአብሔርን ተግ ፭
ሣፅ አታማርር በገሠፀህም ጊዜ ቢዘልፍህ ከእሱ አት
ራቅ ይላችኋልና ። ምዕ፡ ፫ ፲፩ - ፲፪ ።
እግዚአብሔር የሚወደውን ይገሥፃልና፡ የሚወደ ፮
ውን ልጅ ሁሉ ይቀጡታል ። ራእ፡ ዮሐ፡ ፫ ፲፱ ።
መከራችሁን ታገሡ፡ እግዚአብሔር ልጆቹ እንደ መሆ ፯
ናችሁ ይወዳችኋልና አባቱ የማይቀጣው ልጅ ማነው።
ከልቀጧችሁማ በዕዶች ናችሁ ልጆችም አይደላች ፰
ሁም ሁላችሁም ተከክላችኋል፡ መዝ፡ ፸፫ ፲፫-፲፭ ።
በሥጋ የወለዱን አባቶቻችን የሚቀጡን እኛም የም ፱

ፍሮሙ እፎ እንከ ፈድፋደ ንግነይ ወንትአዘዝ ለአበ
መንፈስነ ይደልወነ ወንሕየው ።

ናፍራቸው ከሆነ እንግዲያ በሕይወት እንድንኖር
ለመንፈሳዊ አባታችን በበለጠ ልንታዘዝ ልንገዛ
እንደምን አይገባን ? ዘኍል፥ ፲፯ ፳፪ - ፳፯ ።

፲ ወእሙንቱሰ ለሥላጤ ለኅዳጥ መዋዕል ይጌሥፁነ
በከመ ፈቀዱ ፥ ወውእቱሰ ለእንተ ትኄይስ ለነ ከመ
ንርከብ ቅድሳቲሁ ።

እነሱ ለጥቂት ዘመን ግዳጅ ለመፈጸም እንደ ወደዱ ፲
ይቀጡናል እሱ ግን ክብሩን እንወርስ ዘንድ እኛን
ለምትጠቅም ክብር ይገሥፀናል ። ፩ ጴጥ ፩ ፲፭ - ፲፯ ።

፲፩ ኵሉ ተግሣፅ ኢይመስል ትፍሥሕተ ለጊዜሁ ዳእሙ
ኀዘን ውእቱ ፥ ወድኅረሰ ትፈሪ ሰላመ ለእለ ተገሠፁ
ወተፀሥዮሙ ጽድቀ ።

ተግሣፅ ሁሉ ለጊዜው ያሰዝናል እንጂ ደስ አያሰ ፲፩
ኝም ፥ በኋላ ግን ለተመከሩ ሰላም ታፈራላቸዋለች
ጽድቅንም ትሰጣቸዋለች ። ኢሳ፥ ፶፯ ፲፭ ።

፲፪ ወበእንተዝ አርትዑ እደ ፅውስተ ወእግረ ፅቡሳተ ።

ስለዚህ የሰለለችውን እጅና ያነከሰችውን እግር ፲፪
አቅኑ ። ኢሳ፥ ፴፭ ፫ ።

፲፫ ወግበሩ መንኰራኵረ ርቱዐ ለእገሪክሙ ከመ ይሕ
የው ሕንካሴ ልብክሙ ወኢትትዓቀፉ ።

የልቡናችሁ አንካሰነት እንዲድንና እንዳትጠራጠሩ ፲፫
ለእግራችሁ የቀና መንኰራኩርን አድርጉ ።

፲፬ ወሩፁ ኀበ ሰላም ምስለ ኵሉ ወኢትኅድጉ ቅድሳቲ
ክሙ ወዘእንበሌሁሰ አልቦ ዘይሬእዮ ለእግዚአብሔር።

ከሁሉ ጋር ወደ ሰላም ገሥግሡ ንጽሕናችሁንም አት ፲፬
ተዉ ያለሱ ግን እግዚአብሔርን የሚያየው የለም ።
መዝ ፴፬ ፲፭ ፥ ሮሜ ፲፪ ፲፰ ፥ ፪ ጢሞ ፪ ፳፪ ።

፲፭ አስተሐይጹ አልቦ ዘያሰትት ጸጋ እግዚአብሔር ወአ
ልቦ ዘይትረከብ ሥርው መሪር እንተ ታሠርፅ
ሕማመ እንተ ታስሕቶሙ ወታረኵሶሙ ለብዙኃን ።

አስተውሉ የእግዚአብሔርን ጸጋ የሚያቃልል አይ ፲፭
ኑር መከራን የምታመጣ ብዙዎቹን የምታስታቸ
ውና የምታረክሳቸው የመራር ሥር ሆኖ የሚገኝ
አይኑር ። ዘዳግ ፳፱ ፲፰ ።

፲፮ አልቦ ዘይከውን ዘማዊ ወርኩሰ ከመ ዔሳው ዘሤጠ
ብኵርናሁ ለአሐዱ መብልዕ ።

ላንድ ጊዜ መብል ብሎ ብኵርናውን እንደ ሸጠ ፲፮
እንደ ዔሳው ሴሰኛና ርኩሽ የሚሆን አይኑር ። ዘፍጥ ፥
፳፭ ፴፫ - ፴፬ ።

፲፯ ተአምሩ ከመ ድኅሬሃ ፈቀደ ይረስ በረከተ ወአው
ፅእዎ እስመ ተስእኖ ወኀጥአ ፍኖተ በዘይኔስሕ ወኀ
ሠሣ እንዘ ይበኪ ።

ኋላ ግን በረከትን ሊወርስ እንደ ወደደና እንዳ ፲፯
ወጡት ታውቃላችሁ ፥ መመለስ ተስኖታልና የሚመ
ለስበትንም መንገድ አጥቶአልና እያለቀሰም ፈለ
ጋት ። ዘፍጥ ፳፯ ፴፩ - ፴፪ ።

፲፰ እስመ ኢመጻእክሙ ኀበ እሳት ዘያስተርኢ ዘይነድድ
ወጽልመት ግፍትዕት ወቆባር ወበውሎ ወጣቃ ።

የሚነድ እሳት ወደሚታይበት ወደ ድቅድቅ ጨለማ ፲፰
ወደ ጭጋግ ወደ ጥቅል ነፋስ የሚደሠሥ ወደሚመ
ስል ጨለማ አልመጣችሁምና ። ዘፀአ ፲፱ ፲፪ - ፲፬ ።

፲፱ ወድምፀ መጥቅዕ ወቃለ ነገር ዘሰምዑ እሙንቱ
ወኢፈቀዱ ዳግመ ይትናገሮሙ ።

የነጋሪት ድምፅ ወደ ተሰማበት እነዚያም የነገሩን ፲፱
ድምፅ ሰምተው ዳግመኛ ሊነግራቸው ያልወደዱት
ድምፅ ወደ ተሰማበት ። ዘፀአ ፳ ፲፰ - ፲፱ ።

፳ እስመ ስእንዎ አጽምኦቶ ለዘተናገሮሙ ፥ ወእመኒ
እንስሳ ቀርበ ለውእቱ ደብር ይዌግርዎ ።

የተናገራቸውን ሊሰሙት አልተቻላቸውምና እንስ ፳
ሳም ያንን ተራራ ከቀረበው ይወግሩት ነበር ። ዘፀአ
፲፱ ፲፪ - ፲፫ ።

፳፩ ወዝንቱ ኵሉ በእንተ ውእቱ ግሩም ዘአስተርአዮሙ
ወሙሴኒ ይቤ ርዑድ ወድንጉፅ አነ ።

ይህ ሁሉ ስለ ታያቸው ግሩም ነገር! ነው ሙሴም እኔ ፳፩
ፈርቻለሁ ደንግጬለሁ ብሏል ። ዘዳግ ፱ ፲፱ ።

፳፪ ወአንትሙሰ በጻሕክሙ ኀበ ጽዮን ሀገረ እግዚአብ
ሔር ሕያው ኢየሩሳሌም እንተ በሰማያት ወኀበ
አእላፍ መላእክት ፍሡሓን ።

እናንተ ግን የሕያው እግዚአብሔር አገር ወደም ፳፪
ትሆን ወደ ጽዮን ደስ ብሏቸው የሚኖሩ አእላፍ
መላእክት ወደ አሉበት ወደ ሰማያዊት ኢየሩሳሌም
ደርሳችኋል ። መዝ ፹፰ ፲፰ ። ዳን ፯ ፲ ።

፳፫ ወማኅበረ በኵር እለ ጽሑፍ አስማቲሆሙ በሰማ
ያት ወኀበ እግዚአብሔር መኰንነ ኵሉ ወኀበ መን
ፈስ ጻድቃን ፍጹማን ።

ስማቸው በሰማያት የተጻፈ ማኅበረ በኵር ወዳሉ ፳፫
ባት ፥ ሁሉን የሚገዛ እግዚአብሔር ወዳለበት ፥ በፍጹ
ማን ጻድቃን አድሮ የሚኖር መንፈስ ቅዱስ ወዳለ
ባት ደርሳችኋል ። ሉቃ ፲ ፳ ፥ ራእ ዮሐ ፲፱ ፲፩ ።

፳፬ ወኀበ ኢየሱስ ኀሩይ ወመርሕ ለሐዳስ ሥርዓት ወለ

ለሐዲስ ሥርዓትና በመናገር ከአቤል ደም የሚበልጥ ፳፬

ንዝኀተ ደም ነበበ ዘይኄይስ ተናግሮ እም዗ አቤል፤
ዑቁ እንከ ኢትአበይዎ ለዘተናገረክሙ እምሰማይ ።

፳፭ ሰበ እሙንቱ ኢድኅኑ እስመ አበይዎ ለዘአስተርአ
ዮሙ በደብር አፎ እንከ ፈድፋደ ንሕነ ለእመ ሜጥነ
ገጸነ እምኔሁ ለዘመጽአ እምሰማያት ።
፳፮ ወአድለቅለቃ ለምድር ቃሉ ይእተ አሚረ ወይእዜኒ
ነገረ ወይቤ ዓዲ ምዕረ አነ አድለቀልቃ ለምድር
ወአኮ ለምድር ባሕቲታ ዓዲ ለሰማይኒ ።

፳፯ ወዘይቤ ዓዲ ምዕረ ያሬኢ ከመ ያፈልስ ወያኃልፎ
ለዘያንቀለቅል እስመ ፍጡራን እሙንቱ ከመ ይን
በር ዘኢያንቀለቅል ።
፳፰ ወበእንተዝ ንነሥእ ንሕነ መንግሥተ ዘኢያንቀለቅል
ወብነ ጸጋሁ እንተ በእንቲአሁ ንሠውዕ ለእግዚአብ
ሔር፤ ወናሠምሮ በጸሎት ወበስኢል ወበፍርሃት
ወበረዓድ ።
፳፱ እስመ አምላክነ እሳት በላዒ ውእቱ ።

ምዕራፍ ፲ወ፫ ፤

ክፍል ፲ወ፩ ፡ በእንተ ተወክፎ ነግድ ።

፩ ወሀልወ በተፋቅሮ ምስለ቎ ቢጽክሙ ።

፪ ወኢትርስዑ ተቀብሎ ነግድ እስመ በእንቲአሁ በ
እለ ከፈሉሙ ከመ ይትቀበሉ ነግደ መላእክት እንዘ
ኢየአምሩ ።
፫ ተዘከሩ ሙቁሓነ ዘከመ ተሞቃሕክሙ ምስሌሆሙ
ወእለ ተማቀዩ ከመ ዘሀለውክሙ በሥጋክሙ ።

፬ ክቡር አውስቦ በኵሉ ወለምስካበሙኒ አልቦቱ ስእ
በት፤ ለዘማውያንሰ ወለእለ ያረኵሱ ሥጋሆሙ ይኴ
ንኖሙ እግዚአብሔር ።
፭ ወእንዘ ኢታፈቅሩ ንዋየ ሀልዉ ወበሕቱ የአክለ
ክሙ ዘብክሙ፤ እስመ ውእቱ ይቤ ኢየኀድገከ
ወኢይትሄየየከ ።
፮ ወይእዜኒ ተአሚነነ ንበል እግዚአብሔር ይረድአኒ
ወኢይፈርሀ እንስ እመሕያው ምንተ ይሬስየኒ ።
፯ ተዘከሩ መኳንንቲክሙ ዘነገሩክሙ ቃለ እግዚአብ
ሔር ወእንዘ ትሬእዩ ሠናየ ግእዘሙ ተመሰሉ በሃ
ይማኖቶሙ ።
፰ እስመ ኢየሱስ ክርስቶስ ውእቱ ዘትማልም ወዮም
ወከመ ውእቱ እስከ ለዓለም ።
፱ ኢታምጽኡ ከልአ ነኪረ ትምህርተ እስመ ይኄይስ
ጸጋሁ ያስተፍሥሕ ልበክሙ ወአኮ በመብልዕት ዘኢ
ይበቍዖሙ ለእለ ያንሰስዉ ቦቱ ።
፲ ወብነ ምሥዋዕ ዘኢይከውኖሙ ይብልዑ እምኔሁ
እለ የሐርምዋ ለደብተራ ።



ደምን ለመርጨት መሪ የሆነው አስታራቂ ኢየሱስ
ወደ አለበት ደርሳችኋል፤ እንግዲህ ከሰማይ ወርዶ
የተናገራችሁን እንቢ እንዳትሉት ዕወቁ ። ም ፱ ፲፭ ።
እነሱ በደብረ ሲና የተገለጠላቸውን እንቢ ስላሉት ፳፭
ካልዳኑ እኛማ ከሰማያት ከመጣ ከእሱ ፊታችንን
ከመለስን እንዴት እጅግ አይፈረድብን? ። ም ፪ ፪-፲።
ያን ጊዜ ቃሉ ምድርን አናውጧታል አሁንም እኔ ፳፮
ምድርን እንደገና አናውጣታለሁ የማናውጣትም
ምድርን ብቻ አይደለም ሰማይንም ነው እንጂ ብሎ
ተናግሯል ። ሐጌ ፪ ፯ ።
ዳግመኛም አንድ ጊዜ ማለቱ የሚናወጠውን እንደ ፳፯
ሚያስልፈው ያሳያል ፍጡራን ናቸውና የማይናወ
ጠው ፀንቶ ይኖር ዘንድ ። መዝ ፲፪ ፳፮ ።
ስለዚህም እኛ የማይናወጥ መንግሥትን እናገኛለን ፳፰
ስለ እሱ ለእግዚአብሔር መሥዋዕት የምናቀርብበት
ጸጋው አለን፤ በጸሎትና በምልጃ በፍርሃት በረዓድ
ሆነን ደስ እናሰኘዋለን ። ዳን ፪ ፵፬ ። ፯ ፲፬ ።
ፈጣሪያችን የሚያቃጥል እሳት ነውና ። ዘዳ ፬ ፳፬ ። ፳፱

ምዕራፍ ፲፫ ፤

ክፍል ፲፩ ፡ እንግዳ ስለ መቀበል ።

ከወንድሞቻችሁ ጋር በፍቅር ፀንታችሁ ኑሩ ። ፩
ሮሚ ፲፪ ፲ ። ፪ ጴጥ ፩ ፯ ።
እንግዳ መቀበልን አትርሱ እንግዳ መቀበልን ስለ ፪
ወደዱ ሳያውቁ የመላእክትን እንግድነት ይቀበሉ
ዘንድ ያደላቸው አሉና ። ሮሚ ፲፪ ፫ ።
እብራችኋቸው እንደ ታሠራችሁ አድርጋችሁ እሥ ፫
ረኞችን አስቡ፤ መከራ የሚቀበሉትንም ከነሱ ጋር
በሥጋችሁ እንዳላችሁ ሁናችሁ ። ማቴ፡ ፳፭ ፴፮ ።
መጋባት በሁሉ ዘንድ ክቡር ነው ለመኝታቸውም ፬
ርኵሰት የለውም አመንዝሮችንና አካላቸውን የሚ
ያረክሱትን ግን እግዚአብሔር ይፈርድባቸዋል ።

ያላችሁ ይበቃችኋል እንጂ ገንዘብን አትውደዱ ፭
አልጥልህም ቸል አልልህም ብሏልና ።
አሁንም አምነን "እግዚአብሔር ይረዳኛል ሰው ምን ፮
ያደርገኛል አልፈራም" እንበል ። መዝ ፶፮ ፭፤፪፲፰ ፯።
የእግዚአብሔርን ቃል የነገሯችሁ መምህራኖቻች ፯
ሁን አስቡ፤ በጎ ግብራቸውንም አይታችሁ በሃይማ
ኖት ምሰሏቸው ። ፩ ቆሮ፤ ፬ ፲፮ ።
ኢየሱስ ክርስቶስ ትናንት የነበረ ዛሬም ያለ ወደፊ ፰
ትም ለዘለዓለም የሚኖር ነውና ። ፩ ቆሮ፤ ፫ ፲፩ ።
ሌላ ልዩ ትምህርት አታምጡ ጸጋው ልባችሁን ደስ ፱
ቢያሰኛችሁ ይሻላልና ደስ ማሰኘቱም የሚኖሩበትን
ሰዎች በማይረባቸው መብል መጠጥ አይደለም ።
ደብተራ ኦሪትን ሲያገለግሉ የነበሩ ካህናት ሊበሉ ፲
ለት የማይገባቸው መሥዋዕት አለን? ። ምዕ ፰ ፬-፭።

፲፩ እስመ ዘይሠውዑ እንስሳ ደመ ያበውእ ሊቀ ካህናት
ውስተ ቅድስተ ቅዱሳን በእንተ ኃጢአት ወያውዕ
ይዎ ሥጋሁ በአፍአ እምትዕይንት ።
፲፪ ወበእንተዝ ኢየሱስኒ ከመ ይቀድሶሙ ለሕዝብ
በደሙ በአፍአ እምትዕይንት ተቀትለ ።
፲፫ ወይእዜኒ ንፃእ ኀቤሁ አፍአ እምትዕይንት እንዘ ንፀ
ውር ትዕይርቶ ።
፲፬ ዘአኮ ብነ ዝየ ሀገር ዘይነብር ፡ አላ እንተ ትመጽእ
መንግሥተ ንኅሥሥ ።
፲፭ ቦኑ እንከ ኢይከውነነ ናብእ መሥዋዕተ ስብሐት
በኵሉ ጊዜ ለእግዚአብሔር ፍሬ ከናፍሪነ ከመ ንእ
መን በስሙ ።
፲፮ ወኢትርስዑ ምሕረ ነዳያን ወተሳትፎቶሙ ፡ እስመ
ዘከማሁ መሥዋዕት ይኤድም ለእግዚአብሔር ።

፲፯ ተአዘዙ ለመኳንንቲክሙ ወተኰነኑ ሎሙ እስመ
እሙንቱ ይተግሁ በእንተ ነፍስክሙ ከመ ዘይትሐ
ሰብዎሙ በቅድመ እግዚአብሔር በእንቲአክሙ ከመ
በፍሥሓ ይግበርዎ ለዝንቱ ወኢይንሀኩ ።
፲፰ ወዝንቱ ይደልወክሙ ከመ ትጸልዩ በእንቲአነ ፡ ወን
ትአመን ከመ ታፈቅሩ ወትፈቅዱ ሠናየ ለኵሉ ።

፲፱ ወፈድፋደ ትግበሩ ዘንተ አስተበቍዐክሙ ከመ
ፍጡነ እብጻሕክሙ ።
፳ ወአምላክ ሰላም ዘአንሥኦ እምዉታን ለሊቀ ኖሎተ
አባግዕ በደመ ሥርዓት ዘለዓለም ለእግዚእነ ኢየሱስ
ክርስቶስ ።
፳፩ ያዕንዕክሙ ከመ ትግበሩ ፈቃዶ በኵሉ ምግባረ
ሠናይ እንዘ ውእቱ ይገብር ለክሙ ሥምረቶ በኢየ
ሱስ ክርስቶስ ዘሎቱ ስብሐት ለዓለመ ዓለም አሜን።

፳፪ አስተበቍዐክሙ አኃዊነ ተወከፉ ቃለ ትምህርት
ዘመሀርኩክሙ እስመ በኅፁር አዘዝኩክሙ ።

፳፫ ወአእምሩ ከመ ጢሞቴዎስ እኁነ ዘተፈነወ እምኀ
ቤነ ኀቤክሙ ወእመሰ አፍጠነ መጺአ እሬእየክሙ።
፳፬ አምኁ ኵሎ መኳንንቲክሙ ወኵሎ ቅዱሳነ አምኁ
ክሙ ኵሎሙ እለ በኢጣልያ ።

፳፭ ወጸጋሁ ለእግዚእነ ምስለ ኵልክሙ አሜን ።

ተፈጸመት መልእክት ኀበ ሰብአ ዕብራውያን ፡ ወተፈ
ነወት በእደ ጢሞቴዎስ ወተጽሕፈት በኢጣልያ ።
ወስብሐት ለእግዚአብሔር አሜን ።



የሚሠዉት እንስሳ ነበርና ሊቀ ካህናቱ ኃጢአትን ፲፩
ለማስተሥረይ ደሙን ወደ ቅድስተ ቅዱሳን ያገባል
ሥጋውንም ከከተማ በውጭ ያቃጥሉት ነበርና ።
ስለዚህ ኢየሱስም ወገኖችን በደሙ ይቀድሳቸው ፲፪
ዘንድ ከከተማ በውጭ ተገደለ ። ዮሐ፡ ፲፱ ፲፯ ።
አሁንም ምስቀሉን ተሸክመን ከከተማ ውጭ ወደ ፲፫
እሱ እንውጣ ። ምዕ፡ ፲፩ ፳፮ ።
ከዚህ የሚኖር አገር የለንም ፡ የምትመጣውን መንግ ፲፬
ሥት እንሻለን እንጂ ። ምዕ፡ ፲፩ ፲ ፡ ፲፪ ፳፪ ።
በውኑ በስሙ እናምን ዘንድ የአንደበታችን ፍሬ ፲፭
የሚሆን ሁሉ ጊዜ ለእግዚአብሔር የምስጋና መሥ
ዋዕት ልናቀርብ አይገባንምን ? ። ፩ ጴጥ፡ ፪ ፭ ።
ለድኾች መራራትን ከነሱ ጋር አንድ መሆንን አት ፲፮
ርሱ እንዲህ ያለው መሥዋዕት እግዚአብሔርን ደስ
ያሰኘዋልና ። ፊልጵ፡ ፬ ፲፰ ።
ለመምህሮቻችሁ ታዘዙ ተገዙላቸው እነሱ ስለ ነፍ ፲፯
ሳችሁ ተግተው ያስተምራሉና በእግዚአብሔር ፊት
ስለ እናንተ የሚተሳሰቧቸው እንደ መሆናቸው ይህ
ንም ደስ ብሎአቸው ያደርጉት ዘንድ እንዳያዝኑ ።
ይህም ስለኛ ትጸልዩ ይገባችኋል ዘንድ ለሁሉ መል ፲፰
ካም ነገርን ማድረግ እንደምትወዱና እንደምትሹ
እናምናለን ። ፪ ቆሮ፡ ፩ ፲፪ ።
ይልቁንም ይህን ታደርጉ ዘንድ እማልዳችኋለሁ ፲፱
ፈጥኜ እንድመጣላችሁ ።
ለዘላለም ፀንቶ በሚኖር የሥርዓት ደም የበጎች እረ ፳
ኞች አለቃ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስን ከሙታን
ለይቶ ያስነሣው የሰላም አምላክ ። ኢሳ፡ ፵ ፲፩ ።
በበጎ ምግባር ሁሉ የሚወደውን እንድትሠሩ ያፅ ፳፩
ናችሁ ለዘለዓለም ክብር ምስጋና በሚገባው በኢየ
ሱስ ክርስቶስ ደስ የሚያሰኘውን እሱ እየሠራላ
ችሁ ፡ አሜን ።
ወንድሞቻችን! ያስተማርኳችሁን የወንጌል ትምህ ፳፪
ርት ተቀበሉ ብዬ እማልዳችኋለሁ በጭሩ አዝዣች
ኋለሁና ።
ወንድማችን ጢሞቴዎስ ከእኛ ወደ እናንተ እንደ ፳፫
ተላከ ዕወቁ፡ ፈጥኖም ከመጣ አያችኋለሁ ።
መምህሮቻችሁን ሁሉ ቸር አላችሁ ? በሉ ፡ ቅዱሳ ፳፬
ንንም ሁሉ ፡ በኢጣልያ ያሉ ሁሉ ቸር አላችሁ ?
ብለዋችኋል ።
የጌታችን ጸጋው ከሁላችሁ ጋር ይሁን ፡ አሜን ። ፳፭

በኢጣልያ ተጽፋ በጢሞቴዎስ እጅ ወደ ዕብራውያን
ሰዎች የተላከች መልእክት ተፈጸመች ።
ለእግዚአብሔር ክብር ምስጋና ይሁን ፡ አሜን ።

# መልእክተ ጴጥሮስ ፩ ። ፩ የጴጥሮስ መልእክት ።

ምዕራፍ ፩ ፡

ክፍል ፩ ፡ በእንተ ተዓግሦ መከራ ።

፩ እምጴጥሮስ ልኡክ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ፡ ለኅ
ሩያን ለእለ ሀለዉ ውስተ በሐውርተ ጳንጦስ ወገላ
ትያ ወቀጳዶቅያ ወእስያ ወቢታንያ ።

፪ ለእለ ቀደሙ አእምሮቶ ለእግዚአብሔር አብ በመን
ፈስ ቅዱስ ከመ ይስምዑ በንዝኅተ ደሙ ለኢየሱስ
ክርስቶስ ፡ ሞገስ ወሰላም ይብዛኅ ለክሙ ።
፫ ይትባረክ እግዚአብሔር አቡሁ ለእግዚእነ ኢየሱስ
ክርስቶስ ዘወለደነ በብዝኀ ምሕረቱ ወለተስፋ እንተ
ባቲ ነሐዩ በተንሥኦቱ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ
እምነ ምዉታን ።
፬ ለተዋርሶ ዘኢይበሊ ወዘኢይረኵስ ወዘኢይጸመሂ
ዘዕቁብ ለነ ወለክሙ በሰማያት ።
፭ ለእለ በኀይለ እግዚአብሔር ዕቁባን በሃይማኖት ለመ
ድኀኒት እንተ ድሉት ከመ ታስተርኢ በደኃሪ
መዋዕል ።
፮ ወትትፌሥሑ እስከ ለዓለም ፡ ወባሕቱ ኅዳጠ ሀለወ
ክሙ ይእዜ ትተክዙ በዘይመጽአክሙ መከራ ዘዘ
ዚአሁ ።
፯ ከመ መከራሃ ለሃይማኖትክሙ ዘይትበደር ፈድፋደ
እምወርቅ ንጹሕ ዘበእሳት አመክርዎ ወትትረከቡ
ሀለወክሙ በክብር ወበስብሐት ወበውዳሴ አመ ያስ
ተርኢ ኢየሱስ ክርስቶስ ።
፰ ውእቱኬ ዘታፈቅርዎ እንዘ ኢትሬእይዎ ፡ ወእስከ
ይእዜ ኢርኢክምዎ ፡ ወባሕቱ ተአምኑ ቦቱ ፡ ወይእ
ዜኒ ትትፌሥሑ በፍሥሓ እንተ አልባቲ ማኅለቅት።
፱ ወትነሥኡ በፍጻሜሃ ለሃይማኖትክሙ መድኀኒተ
ነፍስክሙ ።
፲ ይእቲኬ መድኀኒት እንተ ኀሠሥዋ ወዖድዋ ነቢያት
እለ ተነበዩ በእንተ ክብርክሙ ።
፲፩ እንዘ የኀሥሡ ለአይ ወለማእዜ መዋዕል ዘነገረ በእ
ንቲአሁ በላዕሌሆሙ መንፈሱ ለኢየሱስ ክርስቶስ
ወአቅደመ ሰምዐ ከዊነ በእንተ ዘሀለዎ ይሕምም
ክርስቶስ ወበእንተ ስብሐቲሁ ዘእምድኅሬሁ ።
፲፪ እስመ አስተርአዮሙ ወአኮ በርእሰሙ ዘነገሩክሙ
ዘንተ ዘይእዜ ንዜንወክሙ አላ አይድዑክሙ በመን
ፈስ ቅዱስ ዘተፈነወ እምሰማይ እምኀበ ያፈትዎሙ
ለመላእክት ከመ የሐውጽዎ ።

ምዕራፍ ፩ ።

ክፍል ፩ ፡ መከራን ስለ መታገሥ ።

ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስን ከማገለግል ከኔ ከጴ ፩
ጥሮስ የተላከች መልእክት ፡ በጳንጦስ በገላትያ በቀጳ
ዶቅያ በእስያና በቢታንያ አገሮች ላሉ ለተመረጡ
ምእመናን ። ያዕ፡ ፩ ፩ ። ግብ ሐዋ ፪ ፱ ።
እግዚአብሔር አብን አስቀድመው በመንፈስ ቅዱስ ፪
ላወቁት የኢየሱስ ክርስቶስን የደሙን መፍሰስ ይመ
ሰክሩ ዘንድ ሞገስና ሰላም ይብዛላችሁ። ሮሜ ፰ ፳፱።
ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከሙታን ተለይቶ በመነ ፫
ሣቱ ሕይወት ለምናገኝበት ተስፋ በቸርነቱ ብዛት
የወለደን የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ አባቱ እግዚ
አብሔር ይክበር ይመስገን ። ፪ ቆሮ ፡ ፩ ፫ ።
ለእኛናለእናንተበልዕልናየተጠበቀልንየማያልፈውን ፬
የማይለወጠውን የማይጠፋውን ዓለም ለመውረስ ።
በኋላ ዘመን ትገለጥ ዘንድ ተዘጋጅታ ላለችው ድኅነት ፭
በሃይማኖት በእግዚአብሔር ኃይል ለምንጠበቀው ።

እስከ ዘላለም ደስ ይላችኋል ነገር ግን በሚመጣባችሁ ፮
ልዩ ልዩ መከራ አሁን ታዝኑ ዘንድ አላችሁ ።

በሃይማኖታችሁ ምክንያት የሚመጣው መከራ በእ ፯
ሳት ከፈተኑት ከጥሩ ወርቅ ይልቅ እንዲወደድ ኢየ
ሱስ ክርስቶስ በሚገለጥበት ጊዜ በክብር በጌትነት
በምስጋና ትገኙ ዘንድ አላችሁ ። ሚልክ፡ ፫ ፫ ።
እሱም ሳታዩት የምትወዱት ነው ፡ እስከ ዛሬም ድረስ ፰
ታምኑበታላችሁ እንጂ አላያችሁትም አሁንም ፍጻሚ
በሌላት ደስታ ደስ ይላችኋል ። ዮሐ፡ ፳ ፳፱ ።
በሃይማኖታችሁም ፍጻሜ የነፍሳችሁን ድኅነት ታገ ፱
ኛላችሁ ። ሮሜ ፮ ፳፪ ።
ስለ ክብራችሁ ትንቢት የተናገሩ ነቢያት ዞረው የፈ ፲
ለጓት ይህቺ ናት ። ዳን፡ ፱ ፳፫ - ፳፬ ፤ ሉቃ፡ ፲ ፳፬።
የኢየሱስ ክርስቶስ ሕይወቱ መንፈስ ቅዱስ የተና ፲፩
ገረው ለመቼ ቀን ፡ ለመቼ ዘመን እንደሆነ ሲሹ ክር
ስቶስ አስቀድሞ መከራ እንደሚቀበል መከራም ከተ
ቀበለ በኋላ እንደሚነግሥ አስቀድሞ መሰከረ ።
ተገልጦላቸዋልና እኛ ዛሬ የምንነግራችሁን የነገሯ ፲፪
ችሁ ከራሳቸው አንቅተው የነገሯችሁ አይደለም መላ
እክትን እንዲያዩት ከሚያስመኛቸው ከሰማይ በተላከ
በመንፈስ ቅዱስ ተገልጦላቸው ነገሯችሁ እንጂ ።

## ክፍል ፪ ፡ በእንተ ተሰፍዎ ሐዲስ ዓለም ።

፲፫ ወይእዜኒ ቅንቱ ሐቌ ልብክሙ ጥዩቀ ወንቁሐ ተሰ
ፈውዋ ለእንተ ትመጽእ ለክሙ ትፍሥሕት በአስተ
ርእዮቱ ለኢየሱስ ክርስቶስ ።
፲፬ ከመ ውሉድ እለ ይትኤዘዙ እንዘ ኢትትመየጡ
ለእንተ ቀዳሚ ኀጋይክሙ በኢያእምሮ ዘፈተው
ክሙ ።
፲፭ ወበሕቱ በከመ ዘጸውዐክሙ ቅዱስ ውእቱ አንትሙኒ
ኩኑ ቅዱሳነ በኵሉ ግእዝክሙ ።
፲፮ እስመ ጽሑፍ ዘይብል ኩኑ ቅዱሳነ እስመ ቅዱስ አነ።

፲፯ ወእመሰ ለአብ ትጼውዕዎ ለዘይኬንን እንዘ ገጸ ኢይ
ነሥእ በበምግባሪሁ ለለአሐዱ እንዘ ትፈርሁ በኵሉ
መዋዕለ ሕይወትክሙ ወበዘአመንክሙ ሑሩ በቲ ።
፲፰ እንዘ ተአምሩ ከመ አኮ በዘይማስን ብሩር ወወርቅ
ዘተቤዘወክሙ እምውስተ ዘኢይበቍዕ ምግባሪክሙ
ዘተመጠውክሙ እምአበዊክሙ ።
፲፱ አላ በክቡር ደሙ ለክርስቶስ ከመ ዘበግዕ ቅድው
ወንጹሕ ።
፳ ዘተአምረ እምቅድመ ይትፈጠር ዓለም ወአስተርአየ
በደኃሪ መዋዕል በእንቲአነ ።
፳፩ እለ በላዕለ እዴሁ አመነ በእግዚአብሔር ዘአንሥኦ
እምውታን ወስብሐተ ወሀበ ፣ ወይእዜኒ ሃይማኖት
ክሙ ወተስፋክሙ ይኩን በእግዚአብሔር ።
፳፪ አንጽሑ ነፍስተክሙ በትእዛዙ ለጽድቅ ወበሃይማ
ኖትክሙ ከመ ታፍቅሩ ካልአኒክሙ እንዘ ኢትና
ፍቁ በምልአ ልብክሙ ተፋቀሩ ዘበጽድቅ በበ
ይናቲክሙ ጽሩቀ ።
፳፫ ከመ ሰብእ እለ ተወልዱ ፍጹመ አኮ እምዘርእ ዘይ
ደመሰስ አላ እምዘርእ ዘኢይጠፍእ በትእዛዙ ለእግ
ዚአብሔር ዘሀለወ ለዝሉፉ ።

፳፬ እስመ ኵሉ ዘሥጋ ከመ ሣዕር ወኵሉ ክብሩ ከመ
ፍሬ ሣዕር ዘእምከመ የብሰ ሣዕር ይትነገፍ ፍሬሁ ።

፳፭ ወቃሉሰ ለእግዚአብሔር ይነብር ለዓለም ፣ ወዝንቱ
ውእቱ ቃሉ ዘነገርናክሙ ።

### ምዕራፍ ፪ ፡

፩ አሰስልዋ እንከ እምኔክሙ ለኵላ እክይ ወለኵላ
ሕብል ፣ ወለናፍቆ ፣ ወለተሐምዮ ፣ ወለተቃንኦ ።

፪ ወኩኑ ከመ እለ ይእዜ ተወልዱ ሕፃናት ወአፍቅሩ
ሐሊበ ነባቤ ዘአልቦቱ ቱስሕት ከመ በቱ ትልኅቁ
ለድኅነት ።
፫ ወናሁ ጥዕምክሙ ከመ ኄር እግዚአብሔር ወኀቤሁ
ምግባኢክሙ ።



## ክፍል ፪፡ አዲሱን ዓለም ተስፋ ስለ ማድረግ።

አሁንም ወገብ ልቡናችሁን ታጥቃችሁ ነቅታችሁ ፲፫
በኢየሱስ ክርስቶስ መገለጥ የምትመጣላችሁን
ደስታ ተጠባበቋት ። ኤፌ፣ ፫ ፲ ።
እንደሚታዘዙ ልጆች ባለማወቅ ትወዱት ወደ ፲፬
ነበረ ወደ መጀመሪያዪቱ በደላችሁ ሳትመለሱ ።

ነገር ግን የጠራችሁ ቅዱስ እንደሆነ እንዲሁ እናን ፲፭
ተም በሥራችሁ ሁሉ ቅዱሳን ሁኑ ። ሉቃ፡ ፩ ፸፭።
"እኔ ቅዱስ ነኝና ቅዱሳን ሁኑ" የሚል ጽሑፍ አለና። ፲፮
ዘሌዋ፣ ፲፩ ፵፬ ፤ መዝ፡ ፸፩ ፳፪ ።
ለያንዳንዱ በየሥራው ፊት ሳይነሣ የሚፈርድ አብን ፲፯
የምትጠሩት ከሆነ በሕይወታችሁ ዘመን ሁሉ እየፈ
ራችሁ በመናችሁበት ፀንታችሁ ኑሩ ። ግ፡ ሐ፡ ፲፯ ፴፩።
ከአባቶቻችሁ ከወረሳችሁት ከማይረባ ከማይጠቅም ፲፰
ሥራችሁ የተቤዠችሁ በሚጠፋ በወርቅ በብር እን
ዳይደለ ዐውቃችሁ ። ሕዝ ፳ ፲፰ ፤ ፩ ቆሮ፣ ፯ ፩ ።
ያማረ የተወደደ በግ እንደመሆኑ በክበረ በክርስቶስ ፲፱
ደም ነው እንጂ ። ራእ ዮሐ ፭ ፱ ።
ዓለም ሳይፈጠር የታወቀ ፤ በኋላ ዘመን ስለ እኛ የተ ፳
ገለጠ ። ሮሜ ፲፮ ፳፭ ። ገላ ፬ ፬ ።
ቃሉን ሰምተን ከሙታን ለይቶ ባስነሣውና ክብርን ፳፩
በሰጠው በእግዚአብሔር ላመነ አሁንም እምነታች
ሁና ተስፋችሁ በእግዚአብሔር ይሁን። ዮሐ፡ ፲፬ ፮ ።
በእውነተኛው ትእዛዝ በሃይማኖታችሁ ፀንታችሁ ፳፪
ልባችሁን ንጹሕ አድርጉ ፤ ሳትጠራጠሩ በሙሉ ልባ
ችሁ ወንድሞቻችሁን ትወዱ ዘንድ ርስ በርሳችሁ
በፍጹም ፍቅር ተዋደዱ ።
ፍጹም አካል አግኝተው እንደ ተወለዱ ሰዎች ፍጹም ፳፫
ልደትን አግኝታችኋል ፤ ከሚጠፋ ዘር አይደለም ለዘ
ለዓለም ፀንቶ በሚኖረው በእግዚአብሔር ትእዛዝ
ከማይጠፋ ዘር ነው እንጂ ። ዮሐ፡ ፩ ፲፫ ።
ሥጋ የለበሰ ሁሉ እንደ ሣር ነውና ክብሩም ሁሉ ፳፬
እንደ ሣር ፍሬ ነው ፤ ሣር ሲደርቅ ፍሬው እንደሚ
ረግፍ ። ኢሳ ፵ ፮ ። ያዕ ፩ ፲ ።
የእግዚአብሔር ቃል ግን ለዘለዓለም ይኖራል ፣ የነገ ፳፭
ርናችሁ ቃሉም ይህ ነው ። ኢሳ ፵ ፰፡ ሉቃ ፲፮ ፲፯ ።

### ምዕራፍ ፪።

እንግዲህ ክፋትን ሁሉ ፣ ሐሰት መናገርን ሁሉ ፣ ጥር ፩
ጥርን፡ መተማማትን፡ መቃናናትንም ሁሉ ከእናንተ
አርቁ ። ሮሜ ፮ ፬ - ፲፪ ። ፩ ቆሮ፣ ፲፬ ፳ ።
ዛሬ እንደ ተወለዱ ሕፃናት ሁኑ ለሕይወት በእሱ ትጉ ፪
ለምሱ ዘንድ ቅልቅል የሌለበትን የዕውቀት ወተት
ውደዱ ። ማቴ፣ ፲፰ ፫ ፤ ዕብ፣ ፭ ፲፪ - ፲፫ ።
እነሆ እግዚአብሔር ቸር እንደሆነ ዐውቃችኋል መመ ፫
ለሻችሁም ወደ እሱ እንደ ሆነ ። መዝ፡ ፴፬ ፱ ።

፬ ወይእቲ እብን እንተ በኀበ ሰብእ ምንንት ወበኀበ
እግዚአብሔርሰ ኅሪት ወክብርት ።
፭ ወአንትሙኒ ዕንወ ከመ እብን መንፈሳዊ ወኩኑ
ታበተ መንፈሳዌ ለክህነት ቅድስት ወንጽሕት ከመ
ታቅርቡ ወታዕርጉ መሥዋዕተ መንፈሳዌ ዘይሰጠወ
ክሙ እግዚአብሔር በእደዊሁ ለኢየሱስ ክርስቶስ ።

፮ እስመ ከመዝ ጽሑፍ ናሁ እሠይም ውስተ ጽዮን
እብነ ማዕዘንት ኅሪተ ወክብርተ ወዘአምነ ባቲ ኢይ
ትኀፈር ።
፯ ለክሙ ውእቱ ክብር ለእለ ተአምኑ ወለእለሰ ይክ
ሕዱ እብን እንተ መነንዋ ነደቅት ይእቲ ኮነት ውስተ
ርእሰ ማዕዘንት ።
፰ ውእቱኬ እብነ ዕቅፍት ወእብነ ክሕድ ለእለ ይትዓ
ቀፉ በቃሉ ወይክሕድዎ ለዘቦቱ ተፈጥሩ ።
፱ ወአንትሙሰ ፍጥረት ኅሩያን ወታበት ለንጉሥ ወሕ
ዝብ ንጹሕ ወሕዝብ ዘይትሜክሕ ከመ ትንግሩ ሠና
ይቶ ለዘጸውዐክሙ እምጽልመት ውስተ ብርሃነ
ስብሐቲሁ ።
፲ እንዘ ቀዲሙ ኢኮንክሙ ሕዝበ ይእዜሰ ሕዝበ እግ
ዚአብሔር አንትሙ ፡ እንዘ ቀዲሙ ኢኮንክሙ ምሁ
ራነ ፡ ይእዜሰ መሃረክሙ ።
፲፩ አ አኀውየ ፍቁራን አስተበቍዐክሙ ብቍዑኒ ከመ ፈላሲ
ወከመ ነግድ ወከመ ድኩም ታርኅቅዋ ለፍትወተ
ሥጋክሙ እንተ ትፀብአ ለነፍስክሙ ።
፲፪ ወግእዝክሙኒ በማእከለ አሕዛብ ሠናየ ለይኩን ፡ ከመ
ኢይርከቡ በዘይሔምዩክሙ ከመ ገባሬ እኪት ወሠ
ናየ ምግባሪክሙ ይርአዩ ወይሰብሕዎ ለእግዚአብ
ሔር ከመ ይትመየጠሙ ።

፲፫ አትሕቱ ርእሰክሙ ለኵሉ ፍጥረተ እጓለ እመሕያው
በእንተ እግዚአብሔር ወለንጉሥኒ እስመ ኵሉ ሎቱ።
፲፬ ወለመኳንንትኒ እስመ ውእቱ ይፌንዎሙ ከመ ይኰ
ንንዎሙ ለእለ ይገብርዋ ለእኪት ወየአኵትዎሙ
ለእለ ይገብርዋ ለሠናይት ።
፲፭ እስመ ከመዝ ውእቱ ፈቃዱ ለእግዚአብሔር ከመ
በሠናይ ምግባሪክሙ ትእሥሩ አፉሆሙ ለዓብዳን
ሰብእ እለ ኢየአምርዎ ለእግዚአብሔር ።
፲፮ ወኩኑ ከመ አግዓዝያን ወአኮ ከመ እለ በሙ ጌጋይ
ዘእኩይ ።
፲፯ ወአንትሙሰ ከመ አግብርተ እግዚአብሔር ኵሎ አክ
ብሩ ወቢጸክሙኒ አፍቅሩ ፡ ወለእግዚአብሔርኒ ፍር
ህዎ ፡ ወለንጉሥኒ አክብርዎ ።
፲፰ ወአንትሙኒ ነባሪ ተኰነኑ ለአጋእዝቲክሙ እንዘ
ትፈርሁ ወአኮ ዳእሙ ለኄራን ወለመሓርያን አላ
ለእኩያንኒ ።
፲፱ እስመ ጸጋ እግዚአብሔር ትትወሀብ ለዘበእንተ ሠናይ
ምግባሩ ይትዔገሥ ለኃዘን እንዘ የሐምም በግፍዕ

ይህቺ ድንጋይ በሰው ዘንድ የተናቀች ናት ፡ በእግዚ ፬
አብሔር ዘንድ ግን የከበረች የተመረጠች ናት ።
እናንተም እንደ መንፈሳዊ ድንጊያ ዕኑ እግዚአብሔር ፭
በኢየሱስ ክርስቶስ እጅ የሚቀበላችሁን መንፈሳዊ
መሥዋዕትን ታሳርጉ ዘንድ ታቀርቡ ዘንድ ክብርት
ንጽሕት ለሆነችው አገልግሎት መንፈሳዊ ታቦት
ሁኑ ። ኢሳ ፶፮ ፳፬ ። ሆሴ ፲፬ ፭ ። ኤፌ ፡ ፪ ፳፩ ።
እንዲህ ተጽፏልና እነሆ በጽዮን የተመረጠችውንና ፮
የከበረችውን የማዕዝን ድንጊያ አኖራለሁ በእርሷ የሚ
ያምንም አያፍርም ። ኢሳ፡ ፳፰ ፲፮ ።
ክብሩም ለምታምኑ ለእናንተ ነው ፡ በሚክዱት ግን ፯
አናጢዎች የናቋት ድንጊያ እርሷ የማዕዝን ራስ ሆነች።

የዕንቅፋት ድንጊያ እሱ ነው በቃሉ ለሚሰናከሉ የተ ፰
ፈጠሩበት እሱንም ለሚክዱ የክሕደት ድንጊያ ነው ።
እናንተስ የተመረጣችሁ ፍጥረቶች ናችሁ ፡ ለንጉ ፱
ሥም ማደርያ ናችሁ ፡ ንጹሕ ወገን ናችሁ ፡ ከጨለማ
ወደ ክብሩ ብርሃን የጠራችሁን የእሱን ቸርነት ትና
ገሩ ዘንድ የሚመካ ወገን ናችሁ ። ዘፀአ ፡ ፲፱ ፮ ።
ቀድሞ ወገኖቹ አልነበራችሁም ዛሬ ግን የእግዚአ ፲
ብሔር ወገኖች ናችሁ ቀድሞ አልተማራችሁም ነበር
ዛሬ ግን ምሯችኋል ። ሆሴ ፡ ፪ ፳፫ ። ሮሜ ፱ ፳፭ ።
የተወደዳችሁ ወንድሞቼ ! መጻተኛ እንግዳ ደካማ ፲፩
መስላችሁ ነፍሳችሁን የምትወጋትን የሥጋችሁን ፈ
ቃድ ታርቋት ዘንድ እለምናችኋለሁና በጀ በሉኝ ።
አኳኋናችሁም በአሕዛብ መካከል ያማረ ይሁን እንደ ፲፪
ክፉ አድራጊ አድርገው የሚነቅፏችሁ ምክንያት
እንዳያገኙ መልካሙን ሥራችሁን አይተው እግዚአ
ብሔርን ያመሰግኑት ዘንድ ። ወደ እሱም ይመል
ሳቸው ዘንድ ። ማቴ ፭ ፲፮ ።
ለእግዚአብሔር ብላችሁ ለሰው ሁሉ ራሳችሁን ዝቅ ፲፫
አድርጉ ፡ ለንጉሥም ተገዙ ፡ ሁሉ ተሰጥቷልና ።
ለመኳንንትም ታዘዙ ክፉ አድራጊዎችን ሊቀጡ ፲፬
በጎ አድራጊዎችን ሊያከብሩ ንጉሥ ይሰዳቸዋልና ።

የእግዚአብሔር ፈቃዱ እንዲህ ነውና በበጎ ሥራችሁ ፲፭
እግዚአብሔርን የማያውቁትን የሰነፎችን ሰዎች አፍ
ትዘጉ ዘንድ ነውና ። ምዕ ፡ ፫ ፲፮ ።
ከክፋት ነፃ እንደ ሆናችሁ ኑሩ ክፉ ሕሊና የሚያመ ፲፮
ጣው በደል እንዳለባቸው ሰዎች አትኑሩ ።
እናንተስ የእግዚአብሔር አገልጋዮች እንደመሆና ፲፯
ችሁ ሁሉን አክብሩ ፡ ባልንጀራችሁን ውደዱ እግዚ
አብሔር ፍሩት ፡ ንጉሥን አክብሩት ። ሮሜ ፲፪ ፲ ።
እናንተም ቤተ ሰቦች እየፈራችሁ ለጌቶቻችሁ ተገዙ ፲፰
መገዛታችሁም ለደጎችና ለሚራሩት ብቻ አይደለም
ለክፉዎችም እንጂ ። ኤፌ ፡ ፮ ፭ ፤ ቲቶ ፪ ፱ ።
ስለ በጎ ሥራው ሳይበድል እየተበደለ መከራን ለሚ ፲፱
ታገሣት ሰው የእግዚአብሔር ጸጋ ትሰጣለችና ።

፳ ወምንትኑመ ይእቲ እኰቴትክሙ እመ እንዘ ትኤ
ብሱ ትትዔገሡ መቅሠፍተክሙ ፤ አላ እንዘ ሠናየ
ትገብሩ እመ ተፀገሥክሙ ግፍዓክሙ ፤ ዛቲ ይእቲ
እኰቴትክሙ በኀበ እግዚአብሔር ።
፳፩ እስመ በእንተ ዝንቱ ተጸዋዕክሙ እስመ ክርስቶስኒ
በእንቲአክሙ ሐመ ይኅድግ ለክሙ ማዕተበ ከመ
ትትልዉ አሠረ ዚአሁ ።
፳፪ በከመ ውእቱ ኢገብረ ኃጢአተ ወኢተረክበ ሐሰት
ውስተ አፉሁ ።
፳፫ እንዘ ይጼእልዎ ኢጸአለ ወእንዘ ያሐምምዎ ኢተቀ
የመ ፤ አላ አግብአ ለዘይኴንን ጽድቀ ።
፳፬ ወበእንተ ኃጣውኢነ ውእቱ ተሰቅለ ዲበ ዕፅ በሥ
ጋሁ ከመ ያውዕአነ እምኃጣውኢነ ወበጽድቁ ያሕ
ይወነ፤ እስመ በቍስለ ዚአሁ ሐየውክሙ ቍስለ
ክሙ እንዘ ከመ አባግዕ ትስከዉ ።
፳፭ ወይእዜኒ ግብኡ ኀበ ኖላዊክሙ ወዐቃቢሃ ለነፍ
ስክሙ ።

ምዕራፍ ፫ ፤

፩ ወከማሁ አንትንኒ አንስት ተኰነና ለአምታቲክን፤
ከመ እመበ ዘኢየአምን በዝንቱ ነገር እምሥነ ምግ
ባሪሆን ለአንስት ይርአዩ ወዘእንበለ ካሕድ ይርብ
ሕዋ ለነፍሶሙ ።
፪ ወእንዘ ትፈርሃ አሠንያ ግእዘክን በንጽሕ ።
፫ አኮ ከመ ታድልዋ ለዐይነ ሰብእ በተጸፍሮ ሥዕርት
ክን ወአኮ በተሠርግዎ ወርቅ ወብሩር ወአኮ በተላ
ብሶ አልባስ ዘብዙኅ ሤጡ ።
፬ አላ በኅቡእ ልቡ ለሰብእ ለዘኢይጠፍእ ወለዘኢይ
ደምዕ መንፈስ ቅዱስ ዘህልው ቅድመ እግዚአብሔር
ዘብዙኅ ሐሳቡ ።
፭ ወከማሁ ትካትኒ ቅዱሳት አንስት እለ ይትዌከላ ላዕለ
እግዚአብሔር ይሠረገዋ ርእሶን በተኰንኖ ለአም
ታቲሆን ።
፮ ከመ ሣራ እስመ ይእቲ ትትኤዘዝ ለአብርሃም ወእግ
ዚእየ ትብሎ ፤ ወአንትንኒ አዋልዲሃ ኩና በምግባረ
ሠናይ እንዘ ኢትፈርሃ እምነ ድንጋፄ ወኢምንትኒ ።
፯ ወከማሁ አንትሙኒ አደው እንዘ ትነብሩ ምስለ
አንስቲያክሙ ኢታስተሐቅሩ አንስቲያክሙ እስመ
ይደክም ፍጥረተ ዚአሆን ለአንስት፤ አክብሩ አንስቲ
ያክሙ እስመ ይወርሳ እማንቱኒ ክብረ ወሕይወተ
ምስሌክሙ ከመ ኢትትዐቀፍ ጸሎትክሙ ።
፰ ወማኅለቅቱሰ ለኵሉ ከመ ተዐርዩ ልበ በአሐዱ
ሕሊና እንዘ ተሐምሙ ሕማመ ቢጽክሙ ።
፱ ወእንዘ ኢታዐብዩ ልበክሙ ወእንዘ ኢትፈድይዎ
እኪተ ለዘገብረ ለክሙ እኪተ ወእንዘ ኢትጼእልዎ
ለዘጸአለክሙ ፤ ወለጸላኢክሙኒ ባርክዎ እስመ ለዝ
ንቱ ተጸዋዕክሙ ከመ በረከተ ትረሱ ።

፩ የጴጥሮስ መልእክት ።

እየበደላችሁማ የመጣባችሁን መከራ ብትታገሡ ፳
መመስገናችሁ ምንድር ናት ? መልካም እየሠራችሁ
የደረሰባችሁን ግፍ ብትታገሡ ግን በእግዚአብሔር
ዘንድ የምታስመሰግን ይህቺ ናት ። ምዕ ፫ ፲፬ ።
ስለዚሁ ተጠርታችኋልና ክርስቶስም እኩ ፍለጋውን ፳፩
ትከተሉ ዘንድ ምልክቱን ሊተውላችሁ ስለ እናንተ
መከራ ተቀብሏል ። ማቴ፤ ፲፮ ፳፬ ።
እሱ ኃጢአት እንዳልሠራ በአንደበቱም ሐሰት እን ፳፪
ዳልተገኘበት ። ኢሳ፤ ፶፫ ፱፤ ዮሐ፤ ፰ ፵፮ ።
ሲሰድቡት አልተሳደበም መከራ ሲያፀኑበትም አል ፳፫
ተቀየመም ፍርድን ለፈራጁ ሰጠ እንጂ ። ኢሳ፤ ፶፫ ፯።
እሱ ስለ ኃጢአታችን በዕንጨት ላይ ተሰቀለ፤ ከኃ ፳፬
ጢአታችን ያወጣን ዘንድ በቸርነቱም ያድነን ዘንድ
እንደ በጎች ስትቅበዘበዙ በርሱ ቍስል ቍስላችሁን
ድናችኋልና ። ኢሳ ፶፫ ፭፤ ሮሜ ፮ ፲፩፤ ፩ ዮሐ ፫ ፭ ።
አሁንም ወደ እረኛችሁ ወደ ነፍሳችሁ ጠባቂ ተመ ፳፭
ለሱ ። ኢሳ፤ ፶፫ ፮፤ ሕዝ፤ ፴፬ ፭ ።

ምዕራፍ ፫ ።

እንዲሁ እናንተም ሴቶች ለባሎቻችሁ ተገዙ በዚህ ፩
ነገር የማያምን ቢኖር ሴቶች ከሚሠሩት ሥራ ወገን
እንዱን ያዩ ዘንድ ያለ ጥርጥር ሰውነታቸውን ይጠቅ
ሟት ዘንድ ። ኤፌ፤ ፭ ፳፪ ።
እየፈራችሁም በንጽሕና ሥራችሁን አሣምሩ ። ፪
ራስ ፀጕራችሁን በመሠራት ለሰው ይምሰል እንድ ፫
ትሠሩ አይደለም ፤ በወርቅ በብር በማጌጥ አይደለም
ዋጋው ብዙ የሆነ ልብስ በመልበስም አይደለም ።
ሃብቱ ብዙ በሆነ በእግዚአብሔር ህልውና ላለ ለማ ፬
ይለይና ለማይሰማ መንፈስ ቅዱስ ማደሪያ ለመሆን
በሰው በውሥጣዊ ልቡ ነው እንጂ ።
ቀድሞም በእግዚአብሔር ያመኑ ደጋግ ሴቶች ለባሎ ፭
ቻቸው በመገዛት ራሳቸውን ያጌጡ ነበር ።

እንደ ሣራ እሷ አብርሃምን ትታዘዘው ነበርና ጌታ ፮
ዬም ትለው ነበርና፤ እናንተም በበጎ ሥራ ልጆቿ
ሁኑ ፤ ከድንጋፄ የተነሣ ምንም ምን ሳትፈሩ ።
እናንተም ወንዶች ከሚስቶቻችሁ ጋር ስትኖሩ ሚስ ፯
ቶቻችሁን አታቃልሉ ፤ የሴቶች ተፈጥሯቸው ደካማ
ነውና ሚስቶቻችሁን አክብሩ ፤ እነሱም ከእናንተ ጋር
ክብርን ሕይወትን ይወርሳሉና ጸሎታችሁ እንዳት
ሰነካከል ። ኢዮብ ፴፪ ፰ ።
የሁሉም መጨረሻው ግን የወንድሞቻችሁን መከራ ፰
እየተቀበላችሁ በአንድ ሐሳብ ትኖሩ ዘንድ ነው ።
ልባችሁን ሳታስታብዩ ክፉ ላደረገባችሁም ክፉ ሳት ፱
መልሱ የሰደባችሁን ሳትሰድቡ ጠላታችሁን መርቁት
በረከትን ትወርሱ ዘንድ ፤ ለዚህ ተጠርታችኋልና ።

፲ ወዘሰ ያፈቅራ ለሕይወት ወይፈቱ ይርአይ መዋዕለ
ሠናያተ ያርምም ልሳኖ እምእኪት ወከናፍሪሁኒ
ከመ ኢይንብበ ሐሰተ ።
፲፩ ይትገኃሥ እምእኪት ወይግበራ ለሠናይት ፡ ለይኅ
ሥሣ ለሰላም ወይትልዋ ።
፲፪ እስመ አዕይንቲሁ ለእግዚአብሔር ኀበ ጻድቃኒ ወዕ
ዝኒሁ ኀበ ስእለቶሙ ፡ ገጹ ለእግዚአብሔር ኀበ እለ
ይገብሩ እኪተ ።
፲፫ ወመኑ ውእቱ ዘእኪተ ይፈቅድ ለክሙ እመ ትቀ
ንኡ ለገቢረ ሠናይ ።
፲፬ ወእመሰ በገቢረ ጽድቅ ተሐምሙ ብፁዓን አንትሙ
ወዘሰ ይጌርመክሙ ኢትፍርሁ ወኢትደንግፁ አላ
ለእግዚአብሔር ቀድስዎ በኵሉ ልብክሙ ።

፲፭ ወድልዋኒክሙ ሀልዉ በኵሉ ጊዜ ከመ ታውሥእ
ዎሙ ቃለ ለእለ ይሴአሉክሙ በእንተ ዘቲ ተስፋ
ክሙ ።
፲፮ ወበየውሀትክሙ ወበፍርሃተ እግዚአብሔር አሠንዩ
ግእዘክሙ ከመ እመበ እለ ይሔምዩክሙ ከመ ዘእ
ኩይ ምግባሪክሙ ይትኀፈሩ እለ ይሔምዩክሙ እም
ሥነ ምግባሪክሙ ዘበእንተ ክርስቶስ ።

፲፯ እስመ ይኄይስ እንዘ ሠናየ ትገብሩ ወትፈቅዱ ፈቃዶ
ለእግዚአብሔር ትሕምሙ እምነ እንዘ እኪተ ትገብሩ፤

፲፰ እስመ ክርስቶስኒ ምዕረ ሞተ በእንተ ኃጣውአ
ሰብእ ፡ ወበእንቲአነ ሞተ ጻድቅ በእንተ ኃጣውኢነ
ከመ ኪያነ ያብጽሐነ ኀበ እግዚአብሔር ።
፲፱ ሞተ በሥጋ ወሐይወ በመንፈስ።
፳ ወሖረ ኀበ እለ ሙቅሕታ ትነብር ነፍሶሙ ወሰበከ
ሎሙ ግዕዛነ ፡ ለእለ ክሕድዎ ቀዲሙ ወነበሩ በንስ
ሐሆሙ እንዘ ይጸንሑ ትዕግሥቶ ለእግዚአብሔር
ከመ እለ በመዋዕሊሁ ለኖኅ አመ ይገብር ታቦተ ወድ
ኅኑ ባቲ ሰማኒቱ ነፍስ ኅዳጣን እምነ ማየ አይኅ ።
፳፩ ወኪያነኒ ይእዜ ያድኅነነ በአርአያሁ በጥምቀት ፡ አኮ
በሕፅበተ ሥጋ እምርስሐት አላ ከመ ግዕዘ ሠናየ
ይምሐረነ በዘነአምን በእግዚአብሔር ወበተንሥኦቱ
ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ።

፳፪ ዘሀለዎ ይነብር በየማነ እግዚአብሔር ዘዐርገ ውስተ
ሰማይ ፡ ወተኰነኑ ሎቱ መላእክት ፡ ወሥልጣናት ፡
ወኵሉ ኃይል ።

ምዕራፍ ፬ ፤

፩ ወእመሰ ክርስቶስ ተሰቅለ በሥጋሁ በእንቲአነ ወእ
ንትሙኒ ተወልተዉ በይእቲ ሐሊና እስመ ዘሐመ
በሥጋሁ ድኅነ እምኃጣውኢ ።

ሕይወትን የሚወድ መልካም ቀኖችን ሊያይ የሚሻ ፲
እንደበቱን ከክፉ ነገር ይከልክል ፡ ከንፈሮቹንም
ሐሰት እንዳይናገሩ ይከልክል ። መዝ፡ ፴፬ ፲፫ ።
ከክፉ ነገር ይለይ በጎ ሥራን ይሥራ ሰላምን ፈልጎ ፲፩
ይከተላት ።
የእግዚአብሔር ዓይኖቹ ወደ ወዳጆቹ ናቸውና ጆሮ ፲፪
ውም ከልመናቸው ዘንድ ነውና የእግዚአብሔር
ፊቱ ግን ክፉ ወደ ሚሠሩ ሰዎች ናት ።
ለበጎ ሥራ የምትቀኑ ከሆነ ክፉውን የሚወድላችሁ ፲፫
ማነው ? ። መዝ ፴፬ ፲፯ - ፲፯ ።
በጎ ሥራ እየሠራችሁ መከራ ብትቀበሉ ንኡዳን ከቡ ፲፬
ራን ናችሁ ፡ የሚገረምባችሁም ቢኖር አትፍሩ አት
ደንግጡ በፍጹም ልቡናችሁ እግዚአብሔርን አመ
ስግኑት እንጂ ።
ስለዚች ተስፋችሁ ለሚጠይቋችሁ ሰዎች ምላሽ ፲፭
ትመልሱላቸው ዘንድ ሁልጊዜ ተዘጋጅታችሁ ኑሩ ።

በቅንነታችሁ እግዚአብሔርን በመፍራት ሁናችሁ ፲፮
ግብራችሁን አሣምሩ፡ ሥራችሁን ክፉ አስመስለው
የሚያሟችሁ ሰዎች ቢኖሩ ስለ ክርስቶስ ብላችሁ
ከምትሠሩት ከበጎ ሥራችሁ የተነሣ የሚያሟችሁ
ሰዎች ያፍሩ ዘንድ ።
ክፉ ከምትሠሩ ይልቅ በጎ ሥራ እየሠራችሁ የእ ፲፯
ግዚአብሔርን ፈቃድ ፈጽማችሁ መከራ ብትቀበሉ
ይሻላልና ። ቀ፡ ፲፬ ።
ክርስቶስም እኮ ስለ ሰው ኃጢአት አንድ ጊዜ ፲፰
ሙቷል ጻድቁ ስለ እኛ ስለ ኃጢአታችን ሞተ ፡
እኛን ወደ እግዚአብሔር ያደርሰን ዘንድ ።
በሥጋ ሞተ በመለኮት ተነሣ ። ፲፱
አስቀድሞ ከደዉት የእግዚአብሔርን ትዕግሥት ፳
ደጅ እየጠኑ ለነበሩ ሰዎች ነፍሳቸው ታሥራ ወደ
ነበረችበት ሄዶ ነፃነትን ሰበከላቸው፡ ኖኅ መርከብን
በሠራ ጊዜ እንደ አደረገ ከጥፋት ውኃ ጥቂቶች
ስምንት ሰዎች እንደ ዳኑ። ዘፍ ፯ ፲፯ ፤ ኢሳ፡ ፵፪ ፯ ።
እኛንም ዛሬ በዚያው አምሳል በጥምቀት ያድነናል ፳፩
ሥጋን ከእድፍ በማንጻት አይደለም፡ በእግዚአብ
ሔር በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ትንሣኤ በምና
ምን ገንዘብ በጎ ምግባርን ያስተምረን ዘንድ ነው
እንጂ ። ኤፌ ፭ ፳፯ ።
በእግዚአብሔር ቀኝ የሚኖር ወደ ሰማይ ያረገ ፳፪
መላእክት ሥልጣናት ኃይላትም ሁሉ የተገዙለት።
መዝ፡ ፻፲ ፩፤ ሮሚ ፰ ፴፬፤ ኤፌ፡ ፩ ፳ - ፳፩ ።

ምዕራፍ ፬ ።

ክርስቶስ ስለ እኛ በሥጋው ከተሰቀለ እናንተም ፩
በዚች ሐሳብ ተጸረሩ በሥጋው መከራ የተቀበለ ከኃ
ጢአት ድኗልና ። ሮሚ ፮ ፪ ፯ ።

፪ ከመ ኢይሕየው እንከ በፍትወተ ሥጋ አላ በፈቃዱ
ለእግዚአብሔር ይፈጽም ተረፈ ሕይወቱ በሥጋሁ ።

፫ እስመ የአክለክሙ ዘኀለፈ መዋዕል ዘገበርክሙ በቱ
ፈቃዶሙ ለአሕዛብ ፡ ዝሙተ ወፍትወተ ወስክረተ
ወስዋየተ ወስታየ ዘእንበለ ግእዝ ወአፍቅሮ አማ
ልክት ።

፬ ዑቁ እንከ ውስተ ዝንቱ ምግባር ኢትሩፁ ወነኪራነ
ኩኑ እምኔሃ ለይእቲ ፍኖት ወእምነ ውእቱ ምግባር
ዘአልቦ በቁም ፡ ወናሁ ሰብአ እምኔሆሙ ያነክሩ
በእንቲአክሙ ወይፀርፉ ላዕሌክሙ ሰበ ይሬእዩክሙ
ዘኢትሳተፍዎሙ ውስተ ውእቱ ምግባር ዘትክት ።

፭ እሉኬ እለ ሀለዎሙ ያግብኡ ሐሳበ ለዘሀለወ ድልወ
ይኰንኖሙ ለሕያዋን ወለምውታን ።

፮ ወበእንተ ዝንቱ ዜንውዎሙ ለምውታን ከመ ይት
ኰነኑ በሥጋሆሙ በሕገ እጓለ እመሕያው ወይሕ
የዉ በመንፈሶሙ በሕገ እግዚአብሔር ።

፯ እስመ ቀርበ ማኅለቅቱ ለኵሉ አንጽሑ ልበክሙ
ወጸሐዉ ለጸሎት ።

፰ ወእምኵሉሰ ዘይቀድም ተፋቀሩ በበይናቲክሙ በም
ልአ ልብክሙ እስመ ተፋቅሮ ይደፍኖን ወይደመ
ስሶን ለኵሎን ኃጣውእ ።

፱ ወአፍቅሩ ነግደ እንዘ ኢታስተዓፅቡ ።

፲ ወኵልክሙ በከመ ነሣእክሙ ፍቶ ለእግዚአብሔር
በበይናቲክሙ ተለአኩ ከመ ኄር ላእክ እስመ ለለአ
ሐዱ ዘዘዚአሁ ዕሤቱ እምኀበ እግዚአብሔር ።

፲፩ ወለእለሂ ትሜህሩ መሀሩ ቃሎ ለእግዚአብሔር ወዘኒ
ይትለአክ ለይትለአክ በኃይለ እግዚአብሔር ዘወሀበ
ከመ በኵሉ ይሰባሕ እግዚአብሔር በኢየሱስ ክርስ
ቶስ ፡ ዘሎቱ ስብሐት ወኃይል ለዓለመ ዓለም አሜን ።

ክፍል ፪ ፡ ዘከመ ይደሉ ተወክፎ መከራ ።

፲፪ አኀዊነ ኢታንክርዋ ለእንተ ትመጽአክሙ መከራ
ከመ ዘነኪር ግብር ዘይከውን ብክሙ ዳእሙ ይእቲ
ወዘኢትለምዱስ ይበጽሐክሙ ።

፲፫ ዳእሙ ከመ ትሳተፍዎ በሕማሙ ለክርስቶስ ወትት
ፈሥሑ ከመ አመ ያስተርኢ በስብሐቲሁ ትትኃሠዩ
ፍሡሓኒክሙ ።

፲፬ ወእመሰ በ ዘተፀየፉክሙ በእንተ ስሙ ለክርስቶስ
ብፁዓን አንትሙ እስመ ስብሐቲሁ ወኀይሉ ለእግዚ
አብሔር ወመንፈሱ የዓርፍ ላዕሌክሙ ።

፲፭ አልቦ ዘየሐምም እምውስቴትክሙ እው ከመ
ቀታሊ ፡ አው ከመ ሰራቂ ፡ አው ከመ ዘእኩይ ምግ
ባሩ ፡ አው ከመ ዘበዕደ ያፈቅር ወይፈቲ ።



እንግዲህ በሥጋዊ ፈቃድ እንዳይኖር በሥጋው ከሕ ፪
ይወቱ ዘመን የቀረውን በእግዚአብሔር ፈቃድ ይፈ
ጽም ዘንድ እንጂ ።

የአሕዛብ ፈቃድ ዝሙትን ምኞትን ስካርን ተዘርሮ ፫
ማደርን ያለ ልክ መጠጣትን ጣዖት መውደድን ያደረ
ጋችሁበት ያለፈው ዘመን ይበቃችኋል። ኤፌ ፪ ፪-፫።

እንግዲህ ዕወቁ በዚህ ሥራ አትኑሩ ከዚች መንገድ ፬
ልክ መጠን ከሌለውም ከዚህ ሥራ የተለያችሁ ሁኑ
እነሆ ከነሱ ወገን የሆኑ ሰዎች ስለ እናንተ ያደን
ቃሉ በዚህ በቀድሞው ግብራቸው ሳትተባበሩዋ
ቸው ሲያዩዋችሁ ይሰድቧችኋል ።

በሕያዋንና በሙታን ሊፈርድ ለተዘጋጀው ሐሳባቸ ፭
ውን ያበረክቱ ዘንድ ያላቸው እነዚህ ናቸው ።

ስለዚህም በሰው ሕግ በሥጋቸው እንደሚቀጡ በእ ፮
ግዚአብሔር ሕግም በነፍሳቸው እንደሚድኑ ለሙ
ታን ነገሯቸው ። ምዕ፡ ፫ ፲፱ ።

የሁሉም ፍጻሜው ቀርቧልና ልቡናችሁን አንጹ ለጸ ፯
ሎትም ትጉ ። ፩ ቆሮ ፲ ፲፩ ። ፩ ዮሐ ፪ ፲፰ ።

ከሁሉ አስቀድሞ ግን እርስ በርሳችሁ በፍጹም ልቡ ፰
ናችሁ ተዋደዱ ፍቅር ኃጢአቶችን ሁሉ ይሸፍናቸ
ዋል ያጠፋቸዋልና ። ምሳ፡ ፲ ፲፪ ፡ ያዕ፡ ፭ ፳ ።

ሳታንጐራጕሩ እንግዳን ውደዱ ። ዕብ፡ ፲፫ ፪-፮። ፱

ሁላችሁም የእግዚአብሔርን ሃብት እንደ ተቀበላችሁ ፲
መጠን እንደ በጎ አገልጋይ ርስ በርሳችሁ ተረዳዱ ፡
ለያንዳንዱ ከእግዚአብሔር የሚሰጠው ሃብት ልዩ
ልዩ ነውና ።

የምታስተምሩም የእግዚአብሔርን ቃል አስተምሩ ፡ ፲፩
የሚላክም እግዚአብሔር በሰጠው ኃይል ይላክ እግ
ዚአብሔር በኢየሱስ ክርስቶስ በሁሉ ይመሰገን
ዘንድ ጌትነት ክሀሊነት ለዘለዓለም ያለው ፡ አሜን ።

ክፍል ፪ ፡ መከራን መቀበል እንደሚገባ ።

ወንድሞቻችን ! የምትመጣባችሁን መከራ ልዩ ነገር ፲፪
እንደ ተሠራባችሁ አድርጋችሁ አታድንቋት ይህችማ
የለመዳችኋት መከራ ናት የማትለምዱትስ ይመጣ
ባችኋል ። ምዕ፡ ፩ ፮ - ፯ ።

ነገር ግን ክርስቶስን በመከራ ትመስሉት ዘንድ ነው ፲፫
በጌትነቱም በተገለጠ ጊዜ ደስ ይላችሁ ዘንድ ።
ግብ፡ ሐዋ፡ ፭ ፵፩ ፡ ሮሜ ፰ ፲፯ ፡ ያዕ፡ ፩ ፪ ።

ስለ ክርስቶስ ስም የተገዳደሯችሁ ቢኖሩ ብፁዓን ፲፬
ናችሁ የእግዚአብሔር ኃይሉ ክብሩ መንፈሱም ያድ
ርባችኋልና ። ማቴ፡ ፭ ፲፩ ፡ ምዕ፡ ፪ ፳ ።

ከናንተ ወገን እንደ ነፍሰ ገዳይ፡ እንደ ሌባ፡ ወይም ፲፭
እንደ ክፉ አድራጊ፡ ወይም የሌላው የሚሻና የሚ
መኝ ሆኖ መከራ የሚቀበል አይኑር ።

፲፮ ወእመሰ ከመ ክርስቲያናዊ ኢትኀፈሩ አላ ሰብሕዎ
ለእግዚአብሔር በዝንቱ ስም ።
፲፯ እስመ በጽሐ ጊዜሁ ለፍዳ ዘያቀድም እምነ ቤቱ
ለእግዚአብሔር፡ ወእመሰ ከነ እምኅቤነ አቀድሞቱ
ምንተ እንከ ይከውን ደኃሪቶሙ ለእለ ይክሕድዎ
ለወንጌሉ ለእግዚአብሔር ።
፲፰ ወሰበ ጻድቅ እምዕፁብ ይድኅን ኃጥእ ወዐማፂ በአ
ይቴ ያስተርኢ ሀለዎ ።
፲፱ ወእለኒ የሐምሙ በእንተ ፈቃዱ ለእግዚአብ
ሔር ያማኅፅኑ ነፍሶሙ ኀበ ምእመን ፈጣሪ
በገቢረ ሠናይ ።

ምዕራፍ ፭ ፤

፩ ወለእለኒ ይትለኀቁ እምኔክሙ አስተበቍዖሙ አነ
ልኂቅ ከልአሙ ወሰማዕት በእንተ ሕማሙ ለክርስ
ቶስ ዘሀለዎ ያስተርኢ በስብሐቲሁ ።
፪ ከመ ትኩኑ ሱታፌ ረዐዩ ዘሀለወ ኀቤክሙ መር
ዔቶ ለእግዚአብሔር እንዘ ተዐቀብዎሙ ወኢትቅ
ንይዎሙ በኵርህ አላ በጽድቅ በእንተ እግዚአብ
ሔር እንዘ ኢትትሬብኅዎሙ አላ በምልአ ልብክሙ
ወበትፍሥሕት ።

፫ እንዘ ኢትትኴየሉ ሕዝበ አላ አርአያ ኩንዎሙ
ለመርዔቱ ።
፬ ከመ አመ ያስተርኢ እግዚአ ኖሎት ትንሥኡ አክ
ሊለ ስብሐት ዘኢይጸመሂ ።
፭ ወከማሁ አንትሙሂ ወራዙት ተኰነኑ ለእለ ይልሀ
ቁክሙ ወኵልክሙ ተመሀርዋ ለአትሕቶ ርእስክሙ
እስመ እግዚአብሔር ያኀሥሮሙ ለዕቡያን ወያከብ
ሮሙ ለእለ ያቴሕቱ ርእሶሙ ።
፮ አትሕቱ እንከ ርእሰክሙ ታሕተ እዴሁ ለእግዚአብ
ሔር ዕንዕት ከመ ያልዕልክሙ አመ ይሔውጸክሙ ።

፯ ወኵሎ ሐሊናክሙ ግድፉ ላዕሌሁ እስመ ውእቱ
ይሔሊ በእንቲአክሙ ።
፰ ጥበቡ እንከ ወአጥብቡ ልበክሙ እስመ ጸላኢክሙ
ጋኔን ይጥሕር ከመ አንበሳ ወየኀሥሥ ዘይውኅጥ ።

፱ አፅንዑ ቀዊመ በሃይማኖትክሙ እንዘ ተአምሩ ከመ
ሕማሙ ለዝ ዓለም ትረክበሙ ለኵሎሙ አኀዊክሙ
ወአፅንዕዋ ለተፋቅሮ ።
፲ ወእግዚአብሔርሰ ዘበኵሉ ክብር ፀውዐክሙ ውስተ
ዘለዓለም ስብሐቲሁ በኢየሱስ ክርስቶስ፡ ወኅዳጠ
ሐሚመክሙ ውእቱ ይፌጽም ለክሙ ወያፀንዐክሙ
ወያሌብወክሙ ።
፲፩ ውእቱ ዘሎቱ ስብሐት ወኀይል ለዓለመ ዓለም
አሜን ።



ክርስቲያን እንደ መሆናችሁ ግን አትፈሩ በዚህ ስም ፲፮
እግዚአብሔርን አመስግኑት እንጂ ። ፊል፡ ፩ ፳፱ ።
ብድራት ለመክፈል ከእግዚአብሔር ቤት ሰቦች የሚ ፲፯
ያስቀድምበት ጊዜ ይመጣልና ማስቀደሙም ከእኛ
ወገን ከሆነ ግን የእግዚአብሔርን ወንጌል ለሚክዱ
ሰዎች ፍጻሜያቸው ምን ይሆን ? ። ኤር፡ ፳፭ ፳፱ ።
ጻድቅ በጭንቅ የሚድን ከሆነ ኃጢአተኛና ዓመፀኛ ፲፰
በየት ይገለጥ ዘንድ አለው ? ። ምሳ፡ ፲፩ ፴፩ ።
የእግዚአብሔርን ፈቃድ ለመፈጸም መከራ የሚቀ ፲፱
በሉ ሰዎች በጎ ሥራ በመሥራት ሰውነታቸውን
ከታመነ ፈጣሪ ዘንድ አደራ ያስጠብቁ ። መዝ ፴፩ ፮።

ም ዕ ራ ፍ ፭ ።

ከእናንተ መካከል በመዓርግ በዕድሜ የሚበልጡትን ፩
በጌትነቱ ይገለጥ ዘንድ ያለውን የክርስቶስን መከራ
የምመሰክረው እኔ ሽማግሌው ወንድማቸው እማል
ዳቸዋለሁ ። ፪ ዮሐ፡ ፩፤ ሮሜ ፰ ፲፯ ።
ትመስሉት ዘንድ ከእናንተ ዘንድ ያሉትን መንጋዎች ፪
ጠብቁ ስትጠብቋቸው በግድ አትግዙዋቸው ስለ እግ
ዚአብሔር ብላችሁ በውነት ጠብቋቸው እንጂ፡ በፍ
ጹም ልቡናችሁ ደስ ብሏችሁ እንጂ እንጠቀምባቸው
ሳትሉ ። ዮሐ፡ ፳፩ ፲፭፤ ግብ፡ ሐዋ፡ ፳ ፳፰ ።
ሕዝቡን ሳታስጨንቁ ለመንጋው ምሳሌ ሁኗቸው ፫
እንጂ ። ፪ ቆሮ፡ ፩ ፳፬፤ ቲቶ ፪ ፯ ።
የእረኞች ጌታ በተገለጠ ጊዜ የማይጠፋውን የክብር ፬
አክሊል ትቀዳጁ ዘንድ ። ዕብ፡ ፲፫ ፳ ።
እንዲሁ እናንተም ጕልማሶች በመዓርግ በዕድሜ ፭
ለሚበልጧችሁ ታዘዙ ሁላችሁም ትሕትናን ተማ
ሩት እግዚአብሔር ትዕቢተኞችን ያዋርዳቸዋል ራሳ
ቸውን ዝቅ የሚያደርጉትን ያከብራቸዋልና ።
እንግዲህ በጕበኛችሁ ጊዜ ከፍ ከፍ ያደርጋችሁ ፮
ዘንድ ፅኑ ከሆነች ከእግዚአብሔር እጅ በታች ራሳ
ችሁን ዝቅ አድርጉ ። ኢዮ፡ ፳፪ ፳፱፤ ያዕ፡ ፬ ፲ ።
አሳባችሁን ሁሉ በእሱ ላይ ጣሉ እርሱ ስለ እናንት ፯
ያስባልና ። ማቴ፡ ፯ ፳፭፤ ፊልጵ፡ ፬ ፯ ።
እንግዲህ አስተውሉ ልቡናችሁንም አስተዋይ አድ ፰
ርጉ ጠላታችሁ ጋኔን እንደ አንበሳ ያናፋልና የሚው
ጠውንም ይሻልና ። ፩ ተሰ፡ ፭ ፯።
የዚህ ዓለም መከራ ወንድሞቻችሁን ሁሉ እንደም ፱
ታገኛቸው ዐውቃችሁ በሃይማኖታችሁ ፀንታችሁ
ኑሩ ፍቅርንም አፅንታችሁ ያዚት ። ኤፌ፡ ፯ ፲፩ ።
በፍጹም ክብር ወደ ዘለዓለም ጌትነቱ በኢየሱስ ክር ፲
ስቶስ የጠራችሁ እግዚአብሔር ነው፡ ጥቂት መከራ
ተቀብላችሁ እሱ ይፈጽምላችኋል ያፀናችኋል ያለብ
ማችኋል ። ምዕ፡ ፩ ፯ ።
ለዘለዓለም ጌትነት ከሀሊነት ገንዘቡ የሚሆን እሱ ፲፩
ነው በውነት ።

፲፪ ምስለ ስልዋኖስ እኁነ ምእመን በከመ ሐለይኩ
ኅዳጠ ጸሐፍኩ ለክሙ እንዘ አስተበቍዐክሙ ወእ
ከውን ስምዐ ከመ በአማን ስብሐቲሁ ለእግዚአብ
ሔር ዛቲ እንተ ባቲ ትቀውሙ ።
፲፫ ትኤምኀክሙ ቤተ ክርስቲያን ኅሬት እንተ ውስተ
ባቢሎን ዘግብጽ ወማርቆስ ወልድየ ።

፲፬ ትአምኁ በበይናቲክሙ በአምኃ ተፋቅሮ ወተሰና
ዐዉ ኵልክሙ እለ በክርስቶስ ሀሎክሙ ፡ ጸጋ ምስለ
ኵልክሙ ።

መልአት መልእክተ ጴጥሮስ ቀዳሚት ።
ወስብሐት ለእግዚአብሔር አሜን ።

ከታመነው ወንድማችን ከስልዋኖስ ጋር አየማለድ ፲፪
ኳችሁ የፀናችሁባት ይቺ በእውነት የእግዚአብሔር
ክብር እንደ ሆነች እየመሰከርኩላችሁ እንደ አሰብ
ኩት ጥቂት ጻፍኩላችሁ ። ዕብ፡ ፲፫ ፳፪ ።
የግብጽ በምትሆነው በባቢሎን ያለችው ቤተ ክር ፲፫
ስቲያን ቸር አላችሁን? ትላችኋለች ልጄ ማርቆስም
ሰላም ይላችኋል ። ግብ፡ ሐዋ፡ ፲፪ ፲፪ ።
ፍቅር ባለው ሰላምታ እርስ በርሳችሁ ሰላም ተባባሉ ፲፬
በክርስቶስ አምናችሁ ያላችሁ ሁላችሁ በስምምነት
ኑሩ ፡ ጸጋ ከሁላችሁ ጋር ይሁን ።

መጀመርያዪቱ የጴጥሮስ መልእክት ተፈጸመች ።
ለእግዚአብሔር ምስጋና ይሁን ፡ አሜን ።



# መልእክተ ጴጥሮስ ፪ ።

## ምዕራፍ ፩ ፤

### ክፍል ፩ ፥ ዘከመ ይደሉ አትልዎ ሠናይት በሃይማኖት ።

፩ እምኀበ ስምዖን ኬፋ ገብሩ ወልኡኩ ለኢየሱስ ክር
ስቶስ ለእለ ነኀብር ክብረ በሃይማኖት እንተ ከፈለነ
በጽድቁ ለአምላክነ ወፈራቂነ ኢየሱስ ክርስቶስ ።

፪ ሞገስ ወሰላም ይብዛኅ ለክሙ በአእምሮቱ ለአምላክነ
ወኢየሱስ ክርስቶስ እግዚእነ ።

፫ ዘበኀይለ መለኮቱ ወሀበነ ለነ ኵሎ ምግባረ ዘይወስድ
ኀበ ሕይወት ወጽድቅ ውእቱ ዘጸውዐነ ውስተ ስብ
ሐቲሁ ወውስተ ሠናይቱ ።

፬ በዘቦቱ ነሐዩ ወነዐቢ ወንክብር በተስፋሁ እንተ ጸገ
ወነ ከመ በእንተ ዝንቱ ትኩኑ ሱቱፋነ ለመለኮተ
ዚአሁ እንዘ ትጕይይዋ ለፍትወተ ሙስናሁ ለዝንቱ
ዓለም ።

፭ ወአንትሙኒ በኵሉ ጕጕአ ገቢረክሙ አትልውዋ
ለሠናይት በሃይማኖትክሙ ፤ ወበሠናይት ለአእምሮ ፤
ወበአእምሮ ለኢዘምዎ ።

፮ ወበኢዘምዎ ለትዕግሥት ፤ ወበትዕግሥት ለአምልኮ ።

፯ ወበአምልኮ ለተአኀዎ ፤ ወበተአኀዎ ለተፋቅሮ ።

፰ ወዝንቱ ኵሉ እምከመ ሀለወ ኀቤክሙ ኢኮንክሙ
ፅሩዓነ ወኢኮንክሙ እለ እንበለ ፍሬ አላ ያበጽሐ
ክሙ ውስተ አእምሮቱ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ።

፱ ወዘሰ ኢሀሎ ውስተ ዝንቱ ምግባር ዕዉር ውእቱ
ዘየሐውር በመርስስ ወረስዐ አንጽሖ ርእሶ እምእለ
በልዖ በላዕሌሁ ኃጣውኢሁ ።

፲ ወይእዜኒ አኀዊነ ጕጕኡ ከመ በጽንዐ ምግባሪክሙ
ጽንዕተ ትኩን ጽዋዔክሙ ወታወፍዩ ሐሳበ ሃይማ
ኖትክሙ ፤ ወዘንተ እንዘ ትገብሩ ኢትስሕቱ ።

፲፩ ወይትወሀበክሙ ርኊብ ፍኖት ዘይወስድ ወስተ ሕይ
ወት ዘለዓለም ወመንግሥቱ ለመድኀኒነ ኢየሱስ
ክርስቶስ ።

### ክፍል ፪ ፥ በእንተ ኑዛዜ ሞቱ ለጴጥሮስ ።

፲፪ ወበእንተዝ እጽሕቅ ለክሙ ዘልፈ ወአዜክረክሙ
ዘንተ ትእዛዘ እንዘ ፅኑዓን አንትሙ በዘሀለወ ጽድቅ ።

፲፫ ወይመስለኒሰ ከመ ርቱዕ ሊተ አምጣነ ሀሎኩ በዝ
ንቱ ሥጋየ አንቅሕክሙ በዘክሮ ።

# ፪ የጴጥሮስ መልእክት ።

## ምዕራፍ ፩ ።

### ክፍል ፩ ፥ በሃይማኖት በጎነትን መያዝ እንዲገባ ።

የኢየሱስ ክርስቶስ አገልጋዩ ተላኪው ከሚሆን ከስ ፩
ምዖን ጴጥሮስ የተላከች መልእክት በፈጣሪያችን
በአምላካችን በኢየሱስ ክርስቶስ ቸርነት ባደለን በሃ
ይማኖት በሚገኘው ክብር ለምንተባበር ትድረስ ።
አምላካችንና ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስን በማወቅ ፪
ሞገስና ሰላም ይብዛላችሁ ።
በመለኮቱ ኃይል ወደ ሕይወትና ወደ ጽድቅ የሚ ፫
ወስደውን ምግባር ሁሉ የሠራልን ወደ ጌትነቱ ወደ
ቸርነቱ የጠራን እሱ ነው ። ፩ ጴጥ ፥ ፪ ፱ ።
በሰጠን በተስፋው እንድንድን ክፍ ክፍ እንድንልና ፬
እንድንከብር ለዚህ የዚህን ዓለም አጥፊ ፈቃዱን
እየሸሻችሁ ጌትነቱን ለማገልገል ተካፋዮች ትሆኑ
ዘንድ ። ፪ ቆሮ ፥ ፪ ፯ ።
እናንተ ግን በሥራው ሁሉ ትጉላን አድርጋችሁ በሃ ፭
ይማኖት ላይ በጎነትን ያዙ ፤ በበጎነትም ዕውቀትን ፤
በዕውቀትም ንጽሕናን ያዙ ። ገላ ፥ ፭ ፮ ።
በንጽሕናም ትዕግሥትን ፥ በትዕግሥትም አምል ፮
ኮቱን ያዙ ።
በማምለክም ላይ ወንድማማችነትን በወንድማማ ፯
ችነትም ላይ ፍቅርን ያዙ ። ገላ ፥ ፮ ፲ ።
ይህ ሁሉ ከእናንተ ዘንድ ካለ ሥራ ፈቶች አይደላ ፰
ችሁም ፍሬ የሌላችሁም አይደላችሁም ጌታችን ኢየ
ሱስ ክርስቶስን ወደ ማወቅ ያደርሳችኋል እንጂ ።
በዚህ ምግባር ፀንቶ የማይኖር ግን በዳሰሳ የሚሄድ ፱
ዕውር ነው ከዘገዩበት ኃጣውእም ራሱን ማንጻትን
የዘነጋ ነው ። ፩ ዮሐ ፥ ፪ ፱ ።
ወንድሞቻችን ! አሁንም በምግባራችሁ ፅናት ሃይ ፲
ማኖታችሁ የፀናች እንድትሆን የሃይማኖታችሁንም
ግምገማ ታበረክቱ ዘንድ ትጉ ፤ ይህንንም ስታደ
ርጉ አትሳሳቱ ።
ወደ ዘለዓለም ሕይወትና ወደ ጌታችን ኢየሱስ ክር ፲፩
ስቶስ መንግሥት የሚወስድ ሰፊ መንገድ ይሰጣ
ችኋል ።

### ክፍል ፪ ፥ ጴጥሮስ ስለ ሞቱ የተናዘዘው ።

አሁንም ፀንቶ በሚኖረው እውነት ፀንታችሁ ሳለ ፲፪
ይህን ትእዛዝ ሁል ጊዜ ላሳስባችሁ እወዳለሁ ።
ነገር ግን በዚህ ሥጋዬ ሳለሁ በማሳሰብ ላነቃቃችሁ ፲፫
የሚገባ ይመስለኛል ። ፪ ቆሮ ፥ ፭ ፩ ።

፲፬ እስመ አአምር ከመ ፍጥንት ይእቲ ስሳሌ ዚአየ
እምኔክሙ በከመ አይድዐኒ እግዚእየ ኢየሱስ ክር
ስቶስ ።
፲፭ ወዓዲ ጕጕኡ ከመ ተሀሉ ኀቤክሙ ዛቲ ትእዛዝ
ዘልፈ ወከመ ትዘከርዋ እምድኅረ ኅልፈትየ ወከማሁ
ትግበሩ ።
፲፮ እስመ ኢኮነ መኃድምተ ጥበብ ዘተሉነ ወአመርና
ክሙ በቱ ኀይሎ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወም
ጽአቶ ወሀልዎቶ አላ ለሊነ ርኢነ ዕበዮ ዘነሥአ
እምኀበ እግዚአብሔር አብ ክብረ ወስብሐተ ።

፲፯ ወቃል ዘወረደ ላዕሌሁ ዘምሉእ ስብሐተ ወልዕልና
ይቤ ዝንቱ ውእቱ ወልድየ ዘአፈቅር ዘአነ ኀረይኩ።

፲፰ ዘንተ ቃለ ንሕነ ሰማዕናሁ ከመ እምሰማይ ወረደ
ሎቱ እንዘ ሀሎነ ምስሌሁ በደብረ መቅደሱ ።
፲፱ ወብነ ዓዲ ዘእምዝኒ ይቀድም ቃለ ነቢያት ዘያዐ
ውቅ ዘንተ ፡ ወእምከመ ጥቀ ታሜንዩ ገቢረ ወትኔ
ጽርዎ ይከውን ለክሙ ከመ ማኅቶት እንተ ታበርህ
ውስተ መካነ ጽልመት እስከ ታበርህ ለክሙ ዕለት
ወይሠርቅ ለክሙ ቤዝ ውስተ ልብክሙ ዘያበርህ ።

፳ ወዘንተ ባሕቱ ቅድሙ አእምሮ ከመ ኵሉ ተነብዮ
ዘውስተ መጽሐፍ አልቦ ላዕሌሁ ፍክሬሁ ።
፳፩ ወኢይከውን ተነብዮ ግሙራ እምፈቃደ ሰብእ ወኢ
እምሥምረት እጓለ እመሕያው ፡ አላ በመንፈስ ቅዱስ
ነበቡ ቅዱሳን ሰብእ ተፈኒዎሙ እምኀበ እግዚአ
ብሔር ።

ምዕራፍ ፪ ፤

<u>ክፍል ፫ ፡ በእንተ ሐሳውያን መሲሕ ።</u>

፩ ወበ ባሕቱ ሐሳውያን ነቢያት ማእከለ ሕዝብ ከመ
እለ ሀለው ማእከሌክሙ ወውስቴትክሙ እለ ሐሰተ
ይሜህሩ ፡ ወእለ ክሕደ ያበውኡ ለሕርትምና ወይክ
ሕድዎ ለእግዚኦሙ ዘተሣየጦሙ ወያመጽእዎ ላዕሌ
ሆሙ ፍጡነ ለሙስና ወለተሠርዎ ።

፪ ወብዙኃን ሰብእ ይተልውዎሙ ለእሉ በእንተ ፍት
ወተ ዝሙቶሙ ወይፀርፉ ላዕለ ፍኖተ ጽድቅ ።
፫ ወይትከሐዱ በቃል ዘለሊሆሙ ፈጠሩ ወበቱ የሐ
ውሩ ፡ ወደይኖሙሰ እምፍጥረተ ዓለም ዘኢተዐርፍ
ወሕርትምናሆሙ እንተ ኢትዴቅስ ።
፬ ወእግዚአብሔርሰ ለመላእክቲሁ ጥቀ አቢሶሙ ኢመ
ሐኮሙ አላ ወደዮሙ ውስተ ፃዕረ ደይን ዘርሱን
ወመጠዎሙ ይትኰነኑ ወይንበሩ ውስተ ፃዕረ ደይን።

፭ ወለዓለምሰ ቀደምት ኢመሐኮሙ አላ አትረፈ ሰማ



ጌታዬ ኢየሱስ ክርስቶስ እንደ ነገረኝ ከናንተ መለ ፲፬
የቴ ፈጥና እንደ ደረሰች ዐውቃለሁና ። ዮሐ ፳፩
፲፰ - ፲፱ ።
ዳግመኛም ይህች ትእዛዝ ሁል ጊዜ በናንተ ዘንድ ፲፭
እንድትኖር ፡ ከሞትኩትም በኋላ ታስቧት ዘንድ እንደ
አዘዝኳችሁም ታደርጉ ዘንድ ቸኩሉ ።
የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስን ኃይሉን ቅድመ ፲፮
ዓለም መኖሩን ወደ ዓለም መምጣቱን ስናስተምራ
ችሁ የተከተልነው የጥበብ ተረት አይደለምና ከእግ
ዚአብሔር አብ ዘንድ ክብርን ምስጋናን ስለ ተቀበለ
እኛ ራሳችን ጌትነቱን አይተን ነው እንጂ ።
ስለ እርሱ የተሰማው ክብርና ልዕልናን የተመላ ፲፯
ቃልም እኔ የመረጥኩት የምወደው ልጄ ይህ ነው
አለ ። ማቴ፡ ፫ ፲፯ ፤ ፲፯ ፭፤ ሉቃ፡ ፱ ፴፭ ።
በመቅደሱ ተራራ ከሱ ጋራ ሳለን ይህንን ቃል ከሰ ፲፰
ማይ እንደወረደለት ሰምተናል ። ማቴ፡ ፲፯ ፭ ።
ደግሞም ከዚህ የሚቀድም ይህንኑ የሚያስታውቀ ፲፱
የነቢያት ቃል አለን ፡ ሥራችሁን እጅግ አሳምራችሁ
ብትመለከቱት በጨለማ ቦታ ውስጥ እንደምታበራ
ፋና ይሆንላችኋል ፀሐይ እስክምታበራላችሁ የሚያ
በራ የአጥቢያ ኮከብም በልባችሁ ውስጥ እስኪወጣ
ላችሁ ድረስ ። መዝ፡ ፻፲፱ ፻፭፤ ፪ ቆሮ፡ ፬ ፮ ።
ግን አስቀድማችሁ ይህን ብቻ ዕወቁ በመጽሐፍ ያለ ፳
ትንቢት ሁሉ ትርጓሜው በላዩ ላይ እንደሌለ ።
ትንቢት በሰው ፈቃድ ከሰው ምኞት ፈጽሞ አይሆ ፳፩
ንም ቅዱሳን ሰዎች ከእግዚአብሔር ተልከው በመን
ፈስ ቅዱስ ተናገሩ እንጂ ።

ምዕራፍ ፪ ።

<u>ክፍል ፫ ፡ መሲሕ ክርስቶስን ስለሚያሳብሉ ።</u>

ነገር ግን በመካከላችሁ በውስጣችሁ ሐሰትን የሚያ ፩
ስተምሩ ለመዋረድ ክሕደትን በሰው ልቡና የሚያሳ
ድሩ በደሙ የዋጃቸውን ፈጣሪያቸውን የሚክዱ ጥፋ
ትንና መደምሰስን ፈጥነው በላያቸው የሚያመጡ
እንዳሉ ሁሉ መምህራንን የሚያስተባብሉ ሰዎች
በሕዝቡ መካከል ነበሩ ። ማቴ፡ ፳፬ ፲፩፤ ፩ ጢሞ፡ ፬ ፩።
ብዙ ሰዎችም ዝሙታቸውን ስለ መውደድ እነሱን ፪
ይከተሏቸዋል ፡ እውነተኛውንም መንገድ ይነቅፋሉ።
ራሳቸው በፈጠሩት ቃል ይከራከራሉ በዚያውም ፫
ፀንተው ይኖራሉ ፍዳቸውም ዓለም ከተፈጠረ ጀምሮ
የማታርፍ ጥፋታቸው የማያንቀላፋ ነው ።
እግዚአብሔርስ ለመላእክቱ ስንኳ በበደሉ ጊዜ አላ ፬
ዘነላቸውም ፡ የሚነድ ዕኑ ሥቃይ ባለበት ጣላቸው
እንጂ ፡ ዕኑ ሥቃይ ባለበት ይኖሩም ዘንድ ለቅጣት
አሳልፎ ሰጣቸው ።
ለቀደሙትም ሰዎች አላዘነላቸውም ፡ እውነትን ያስ ፭

ኒተ ነፍሰ ምስለ ኖኅ ዘዐቀበ ለጽድቅ ከመ ይኩን
ዜናዌ በጽድቅ ወለባዕዳንሰ ሰብአ ረሲዓን ፈነወ
አይኅ ላዕሌሆሙ ።
፮ ወለአህጉረ ሰዶምኒ ወገሞራ አውዐዮን ወገፍትዖን
ወከመዝ ኰነኖሙ ወአርአየ ረሰዮሙ ለእለ በድኅሬ
መዋዕል ለኃጥአን ።
፯ ወለጻድቅሰ ሎጥ ዘይትገፋዕ እምእለ ይኤብሱ በምግ
ባረ ዝሙቶሙ አድኀኖ ።
፰ ወእንዘ ይሬኢ ወይሰምዕ ወኅዱር ምስሌሆሙ ወዕ
ለተ እምዕለት ያኄዕርዋ ለነፍሱ ጻድቅት በእከየ
ምግባሮሙ ።
፱ ናሁኬ አእመርነ ከመ እግዚአብሔር ይክል አድኅኖ
ቶሙ እምነ መንሱት ለጻድቃን፤ ወለኃጥአንሰ ዕለተ
ደይን ትጸንሖሙ ለተዕዕሮ ።
፲ ወፈድፋደሰ ለእለ ይተልውዋ ድኅሬሃ ለፍትወቶሙ
ወያጌምንዎ ለሥጋሆሙ ወያስተሐቅርዎ ለፈጣሬ
ሆሙ ፤ ኅቡላን ወዝሉፋን እለ ኢይደነግፁ ከመ ይዕ
ርፉ ላዕለ ስብሐቲሁ ።
፲፩ ዘውእቱ ኅበ መላእክት እለ ልዑላን እሙንቱ እም
ኔሆሙ በኀይል ወበጽንዕ ወኢይክሉ ተዐግሦ ከመ
ያብጽሑ ላዕሌሆሙ ደይነ ዕርፈቶሙ ።
፲፪ ውእቶሙኬ ከመ እንስሳ ዘአልበ ቃል ዘይትወለድ
ለሙስና ወለተሠርዎ እስመ ይፀርፉ ላዕለ ዘኢየአ
ምሩ ለሕርትምናሆሙ፤ ወሎሙ በሙስናሆሙ ዐሥበ
ዐመፃ ።
፲፫ ወአስተሐወዝዋ ለተደልዎ ስቃየ ዕለቶሙ ወይበ
ልዑ እንዘ ሕብቁቃን ወርኩሳን እለ ኢይጼግቡ ወይ
ትጕሐለዉ በፍቅሮሙ ወይትሜክሑ ለቢጾሙ ከመ
ዘሠናይ ምግባሮሙ ።
፲፬ ወምሉእ ውስተ አዕይንቲሆሙ ዝሙት ወኀጢአት
እንተ አልባቲ ዘይገሀግሃ ፡ ወያደነግፁ ነፍሰ ሰብእ
እለ ስጡሕ ልቦሙ ወትዕግልት ምግባሮሙ ወየኀ
ድጉ መርገመ ለውሉዶሙ ።
፲፭ ወስሕትዋ ለፍኖተ ጽድቅ ወተለውዋ ለፍኖተ በለ
ዓም ወልደ ባሶር ዘአፍቀራ ለዐስበ ዐመፃ ።

፲፮ ወተዘለፎ ለበለዓም በኀጢአቱ ዘኢይነብብ አድግ
በቃለ እጓለ እመሕያው ተናገረ ወከልኦ ለነቢይ
ዕበዲሁ ።
፲፯ እሉ እሙንቱ ዐዘቅት ንጽፍት ወጊሜ ዘነፋስ ይዘ
ርዎ እለ ለደይነ ጽልመት ዘለዓለም የዐቅብዎሙ ።
፲፰ እስመ ዐበይተ ጌጋይ˜ነበቡ ወያደነግፁ ነፍሰ ሰብእ
በእንተ ፍትወተ ዝሙቶሙ ዘሥጋሆሙ ፡ ሰብአ እለ
ኅዳጠ አምሰጡ ወገብኡ ውስተ ጌጋይ ።

፲፱ እለ ሕገ ግዕዛን ተምህሩ ወለሊሆሙኒ ቅኑያን ለሕር
ትምና እስመ ዦሉ˜ለዘተአዘዘ ውእቱ ይትቀነይ ።

ትምር ዘንድ እውነትን ከጠበቃት ከኖኅ ጋር ስምንት
ነፍስ አስቀረ እንጂ እሱን የዘነጉት ሌሎች ሰዎች ግን
ጥፋትን አመጣበቸው ። ዘፍጥ፡ ፫ ፲፫ ።
የሰዶምንና የገሞራንም አገሮች አቃጠላቸው ገለበጣ ፮
ቸው እንዲህ ፈረደባቸው፤ በኋላ ዘመን ለሚኖሡ
ኃጥአንም ምሳሌ አደረጋቸው ። ዘፍጥ፡ ፲፱ ፳፬ ።
በዝሙት ሥራቸው ከሚበድሉት ሰዎች ይገፋ የነበ ፯
ረውን ደገኛው ሎጥን ግን አዳነው ።
ኢብሮዋቸው እየኖረ ሲያይ ሲሰማ ከዕለት ወደ ዕለት ፰
ደገኛዪቱ ነፍሱን በክፉ ሥራቸው ያስጨንቋት ነበር።
መዝ ፻፲፱ ፻፶፫ ። ሕዝ ፱ ፬ ።
እንግዲህ እግዚአብሔር ጻድቃንን ከመከራ ሊያድና ፱
ቸው እንደሚችል እነሆ ዐወቅን ኃጥአንን ግን ፍዳን
ለመቀበል የፍርድ ቀን ትጠብቃቸዋለች ።
ይልቁንም ምኞታቸውን ተከትለው ሰውነታቸውን ፲
የሚያረክሱትን ፈጣሪያቸውን የሚያቃልሉትን ደፋ
ሮችን ተሳዳቢዎችን በጌትነቱ ላይ የስድብ ቃል ሲና
ገሩ የማይደነግጡትን የፍርድ ቀን ትጠብቃቸዋለች ።
ስድባቸውም በኃይል በብርታት ከነሱ በላይ በሚሆኑ ፲፩
በመላእክት ላይ ነው በእነሱ ላይ የስድባቸውን ብድ
ራት ያደርሱባቸው ዘንድ መታገሥ አይችሉም ።
እነሱማ ፈርሶ በስብሶ ለመቅረት እንደሚወለድ ቃል ፲፪
እንደሌለው እንስሳ ናቸው ጥፋት ሊመጣባቸው የማያ
ውቁትን ይሰድባሉና ለእነሱ በጥፋታቸው የዓመፅ
ዋጋ አላቸው ። ኤር፡ ፲፪ ፫፤ ይሁ ቍ፡ ፲ ።
በዕለት መጠጣቸው መደሰትን አጣፍጠው ይዘዋ ፲፫
ታል፤ እየሳቡ ይበላሉ የማይጠግቡ ርኩሳን ናቸው፤
በፍቅራቸው ይሸነጋገላሉ በጎ እንደሚሠሩ ሁሉ ለባ
ልንጀሮቻቸው ይመካሉ ።
በዓይኖቻቸውም የሚያርቃት የሌለ ዝሙት ኃጢአት ፲፬
የተመላ ነው ገራገር የሆነውን የሰውን ልብ ያሸ
ብራሉ፤ ሥራቸው ቀሚያ ነው፤ ለልጆቻቸው መር
ገምን ያተርፋሉ ።
የእውነት መንገድንም ሳቷት የዓመፅን ዋጋ የወደ ፲፭
ዳት የባሶር ልጅ የበለዓምን መንገድ ተከተሉ ።
ዘኍል ፳፪ ፮ ። ራእ ዮ ፪ ፲፬ ።
በኃጢአቱ በለዓምን የማይናገር አህያ በሰው አነጋ ፲፮
ገር ተናግሮ ነቢይን ዘለፈው ስንፍናውንም ከለከለው።
ዘኍል ፳፪ ፳፰ ።
የደረቀች ጕድጓድ ነፋስ የሚበትነው ጉም ለጨለማ ፲፯
ፍርድ የሚጠብቃቸው እሊህ ናቸው ።
ጥቂት ቀን ቈይተው ወደ ኃጢአት የተመለሱ እሊህ ፲፰
ከኃጢአት ታላላቆቹን ተናግረዋልና በሥጋቸው ስለ
ሚሠሩት የዝሙት ምኞት የሰውን ልቡና ያሸብ
ራሉ ።
የነፃነትን ሕግ ተምረው ራሳቸው ለኃጢአት የሚ ፲፱
ገዙ ናቸው ሁሉ ለታዘዘለት ይገዛልና። ዮሐ፡ ፰ ፴፬።

፳ እስመ ጐዩ እምኃጢአቱ ለዝንቱ ዓለም በአእምሮቱ ለእግዚእነ ወመድኃኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወገብኡ ዳግመ ወተጸፍሩ ወተቀንዩ ሎቱ ወይከውኖሙ ደኃሪ ጌጋዮሙ እምነ ቀዲሙ ዘየአክዮሙ ።

፳፩ እምኀየሰሙ ሰበ ኢያእመርዋ ለፍኖተ ጽድቅ እም ያእምርዋ ወይግብኡ ድኅሬሆሙ እምእንተ ተውህ በት ሎሙ ትእዛዝ ቅድስት ።

፳፪ ወበጽሐቶሙ አምሳል እንተ መሰሉ በጽድቅ እንተ ይቤ ከልብ ገብአ ዲበ ቅያኡ፣ ወሐራውያኒ ተኀፂበ ገብአት ዲበ ጸብር ።

## ምዕራፍ ፫፤

### ክፍል ፩፣ በእንተ እለ የሐውሩ በፍትወተ ልበሙ ።

፩ ወዛቲ ይእቲ ካልእትየ ዳግሚትየ ጸሐፍኩ ለክሙ መጽሐፈ ከመ እንሥእክሙ በዘከሮ ወትዕቀብዋ በልብክሙ ለጽድቅ ።

፪ ወከመ ትዘክሩ ቃለ ነቢያት ቀደምት ቅዱሳን ዘይቤሉ ወትእዛዘ እግዚእነ ወመድኅኒነ ኢየሱስ ክርስ ቶስ ዘአዘዘ ለነ ለሐዋርያት ።

፫ ወዘንተኒ ቅድሙ አእምሮ ከመ ሀለዎሙ ይምጽኡ በደኃሪ መዋዕል መስተዓብዳን ለአስተዐብዶ፣ እለ የሐውሩ በፍትወተ ልበሙ ወይብሉ አይቴ ውእቱ ቃሉ ዘይቤ ከመ ሀለዎ ይምጻእ ።

፬ ናሁ እመሰ አበዊነ ቀደምት ሞቱ እስመ ኵሉ ግብር ሀለወ በከመ ሀሎ እምፍጥረተ ዓለም ።

፭ ወኢየአምርዎ ለዝንቱ ከመ ሰማያትኒ ተፈጥራ እም ትካት ወምድርኒ እምነ ማይ ወበማይ ፀንዐት በቃለ እግዚአብሔር ።

፮ ወዓለመ ትካትኒ በቱ አጥፍአ በማየ አይኅ ።

፯ ወይእዜኒ ሰማይ ወምድር በውእቱ ቃል ዝጉባን ወዕቁባን እሙንቱ እስከ ዕለተ ደይን ወድምሳሴ ኃጥኣን ሰብእ ።

፰ ወዘንተ ባሕቱ ኢትርስዑ አኀዊነ እስመ አሐቲ ዕለት በኀበ እግዚአብሔር ከመ ዐሠርቱ ምእት ዓመት፣ ወዐሠርቱ ምእት ዓመት ከመ አሐቲ ዕለት ።

፱ ኢያጐነዲ እግዚአብሔር ቃለ ዘነበበ እስመበ እለ ይብሉ ከመ ይጐንዲ ወባሕቱ ይትዔገሥ በእንቲአ ሆሙ እስመ ኢይፈቅድ መንሂ ያማስን አላ ይነስሑ ለኵሉ ሰብእ ያርኀብ ።

፲ ወዕለቱሰ ለእግዚአብሔር ግብተ ትመጽእ ከመ ሰራቂ፣ እንተ ባቲ ሰማያትኒ ይትረኀዋ ወይሴስላ ወኵሉ ፍጥረት ዘቀዲሙ በውዕየተ እሳት ይትመሰው ወም ድርኒ ወኵሉ ዘላዕሌሃ ግብር ይውዒ ።

ጌታችን መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስን በማወቅ ፳
ከዚህ ዓለም ኃጢአት ከተለዩ በኋላ እንደገና ተመ ልሰው በኃጢአት ተተብትበው ተገዙለት የኋለኛው በደላቸው ከፊተኛው የሚከፋባቸው ይሆናል ።

አውቀዋት ከተሰጠቻቸው ከክብርት ትእዛዝ ወጥ ፳፩
ተው ወደ ኋላቸው ከሚመለሱ ይልቅ የቅንን መንገድ ባያውቋት በተሻለ ነበር ። ሉቃ፣ ፲፪ ፵፯ - ፵፰ ።

"ውሻ ወደ ትፋቱ ተመለሰ፣ እርያም ታጥባ ወደ ፳፪
ጭቃ ተመለሰች" ብለው የመሰሉት ምሳሌ በእ ውነት ደረሰባቸው ።

## ምዕራፍ ፫ ።

### ክፍል ፩፣ ልባቸው በፈቀደው ስለ ሚሄዱ ሰነፎች ።

ወንድሞቼ! ጽድቅን በልባችሁ ትጠብቋት ዘንድ በማ ፩
ሳሰብ እቀሰቅሳችሁ ዘንድ መጽሐፍ አድርጌ የጻፍኩ ላችሁ ሁለተኛዪቱ መልእክት ይህች ናት ።

የቀደሙ ቅዱሳን ነቢያት ያሉትንና ጌታችን መድኃ ፪
ኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ለእኛ ለሐዋርያቱ ያዘዘንን ትእዛዝ ታስቡ ዘንድ ።

ይህንንም አስቀድማችሁ እወቁ በኋላ ዘመን ልባቸው ፫
በወደደው የሚሄዱ ሰነፊው የሚያሰንፉ ሰዎች ይመጡ ዘንድ እንዳላቸው ይመጣ ዘንድ እንዳለው የተናገረው ቃሉ የት አለ? የሚሉ ። ፩ ጢሞ፣ ፬ ፩ ።

እነሆ የቀደሙ አባቶቻችን ሞቱ ዓለም ከተፈጠረ ፬
ጀምሮ የተፈጠረው ፍጥረት ሁሉ እንደፀና አለ ። ኢሳ ፷ ፲፱ ። ሕዝ ፲፪ ፳፩ ።

ሰማያት አስቀድመው እንደተፈጠሩ ምድርም በውኃ ፭
ላይ እንደተፈጠረች በውኃውም ላይ በእግዚአብሔር ቃል እንደፀናች ይህን አያውቁትም ። ዘፍ ፩ ፩፤ ፪ ፯ ። መዝ ፳፬ ፪ ። ማቴ፣ ፳፬ ፴፰ ።

የቀደመውን ዓለም በጥፋት ውኃ አጠፋ ። ዘፍ ፯ ፳፩ ። ፮

አሁንም ሰማይና ምድር፣ ኃጢአተኞች ሰዎች እስከ ፯
ሚጠፉበት እስከ ፍርድ ቀን ድረስ በዚያ ቃል ተመ ዝግበው የሚጠበቁ ናቸው ።

ነገር ግን ወንድሞቻችን! በእግዚአብሔር ዘንድ አን ፰
ዲቱ ቀን እንደ ሺሕ ዓመት፣ ሺሑም ዓመት እንደ አንዲት ቀን እንደሆነች ይህን አትርሱ ።

እግዚአብሔር የተናገረውን ቃል አያስቀርም እን ፱
ዲቀር የሚናገሩ አሉና፣ ነገር ግን ስለነሱ ይታገ ሣል ማንንም ማንን ያጠፋ ዘንድ አይሻምና ንስሐ ይገቡ ዘንድ ለሰው ሁሉ ዕድሜን ይሰጣል እንጂ ።

እግዚአብሔር የሚመጣበትስ ቀን እንደሌባ ድንገት ፲
ትመጣለች ሰማያት ፈጽመው የሚያልፉበት ቀድሞ የነበረው ፍጥረት ሁሉ በእሳት መቃጠል ይጠፋል ምድርም በእሷ ላይ ያለውም ፍጥረት ሁሉ ያልፋል ። ፪ ተሰ ፭ ፪ - ፫ ። ማቴ ፳፩ ፳፱ ። ራእ ዮ ፳ ፲፩ ።

፲፩ ወዝንቱ ኵሉ ተመሲዎ ኀጕኡ ከመ ተሀልዉ በምግባር ቅዱስ ዘጽድቅ ።
፲፪ እንዘ ትሴፈዉ ዕለተ ምጽአቱ ለእግዚአብሔር እንተ ባቲ ሰማያትኒ ይረስና ወይትመሰዋ ወኵሉ ፍጥረት ይውዒ ወይትመሰው ።
፲፫ ሐዳሳተ ሰማያተ ወሐዳሳተ ምድረ ንሴፎ ዘውስቴቶን የኀድር ጽድቅ ።
፲፬ ወይእዜኒ አኀውየ ዘንተ እንዘ ትሴፈዉ ጕጕኡ ይርከብክሙ ዘእንበለ ርስሐት ወዘእንበለ ጌጋይ እንዘ ትሰነአዉ ።
፲፭ ወትዕግሥቱሰ ለእግዚእነ የሀብክሙ መድኀኒተ በከመ እኁነ ጳውሎስ ዘናፈቅር ጸሐፈ ለክሙ በእንተ ዘወሀበ እግዚአብሔር ጥበበ ።
፲፮ ዘከመ ሀሎ ውስተ ኵሉ መጻሕፍቲሁ ዘነበበ ውስቴቶን በእንቲአሁ ለዝንቱ፡ ወዘሰ ነበቡ እሙራን ሰብእ እለ ይሌብውዎ ወእለሰ አልቦሙ ትምህርት እለ ኢለበዉ ይመይጥዎ ለቃለ መጽሐፍ ከመ ሚጥዎን ለብዙኃት መጻሕፍት ለማዕዘሙ ወያማስኑ ።
፲፯ ወአንትሙሰ አኀዊነ አቅድሙ አእምሮ ወተዓቀቡ ከመ ኢትስሐቱ በዘኢይበቍዕ ትምህርት ከመ ኢትደቁ እምነ ምጽናዕክሙ ።
፲፰ ተበዝኁ በእግዚእነ ወበአእምሮቱ ለኢየሱስ ክርስቶስ መድኃኒነ ወእግዚአብሔር አብ፡ ዘሎቱ ስብሐት ይእዜኒ ወዘልፈኒ ወለዓለመ ዓለም አሚን ።

መልአት መልእክተ ጴጥሮስ ዳግሚት ።
ወስብሐት ለእግዚአብሔር አሜን ።



ይህ ሁሉ ከፈለ በኋላ የተቀደሰ የጽድቅን ሥራ በመሥራት እንድትኖሩ ቸኵሉ ። ፲፩
ሰማያት ቀልጠው የሚጠፉበትን ፍጥረት ሁሉ ተቃጥሎ የሚጠፋበትን የእግዚአብሔር ቀን ተስፋ አድርጋችሁ ። ፲፪
ጽድቅ አድሮባቸው የሚኖረውን አዳዲሶቹን ሰማያትንና አዲሲቱን ምድር ተስፋ እናደርጋለን ። ፲፫
አሁንም ወንድሞቼ! ይህን ተስፋ አድርጋችሁ በአንድነት ርኵሰት በደል የሌለባችሁ ሁናችሁ ያገኛችሁ ዘንድ ቸኵሉ ። ፲፬
የጌታችን ትዕግሥቱም ድኅነትን ይሰጣችሁ፡ እግዚአብሔር ዕውቀቱን ስለ ሰጠው የምንወደው ወንድማችን ጳውሎስ እንደ ጻፈላችሁ ። ሮሜ ፪ ፬ ። ፲፭
የዚህን ነገር በተናገረባቸው መጻሕፍቱ ሁሉ እንዳለ የታወቁ ሰዎች የሚናገሩት የተረዱት ናቸው ትምህርት የሌላቸው ያላስተዋሉ ግን የመጽሐፉን ቃል ይለውጡታል ብዙዎችን መጻሕፍት ለማብራቸው እንዲስማማ አድርገው እንደለወጧቸውና እንደ አጠፏቸው ። ፲፮
ወንድሞቻችን! እናንተ ግን በማይጠቅም ትምህርት እንዳትሳሳቱና ፀንታችሁ ከኖራችሁበት ከሃይማኖታችሁ እንዳትወድቁ አስቀድማችሁ ተጠንቀቁ ። ፲፯
በጌታችን አጋዥነት በዝታችሁ ኑሩ መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስንና እግዚአብሔር አብን በማመስገን ክብር ምስጋና ለሱ ይሁን ዛሬም ዘወትርም ለዘለዓለሙ አሜን ። ፲፰

ሁለተኛዪቱ የጴጥሮስ መልእክት ተፈጸመች ።
ለእግዚአብሔር ምስጋና ይሁን፡ አሜን ።

# መልእክተ ዮሐንስ ፩ ።

## መልእክተ ዮሐንስ ሐዋርያ ወልደ ዘብዴዎስ ቀዳማዊ ።

ምዕራፍ ፩ ፤

### ክፍል ፩ ፤ በእንተ ቀድምናሁ ለእግዚአብሔር ።

፩ ንዜንወክሙ በእንተ ውእቱ ዘሀሎ እምቀድም ውእቱ
ዘሰማዕናሁ በዕዘኒነ ወዘርኢናሁ በአዕይንቲነ ወዘጠየ
ቅናሁ ወዘገሠሣሁ እደዊነ በእንተ ነገረ ሕይወት ።
፪ እስመ ሕይወት ተዐውቀት ለነ ወርኢናሃ ወስምዐ
ከነ ወንዜንወክሙ ንሕነ ሕይወተ እንተ ለዓለም
እንተ ሀለወት ኀበ አብ ወተዐውቀት ለነ ።
፫ ወርኢናሃ ወሰማዕናሃ ወንዜንወክሙ ለክሙኒ ከመ
አንትሙኒ ትኩኑ ሱታፌ ምስሌነ ፤ ወሱታፌነሰ
ምስለ አብ ወምስለ ወልዱ ኢየሱስ ክርስቶስ ።
፬ ወዘንተ ንጽሕፍ ለክሙ ከመ ትፍሥሕትክሙ ፍጽ
ምተ ትኩን ብነ ።
፭ ወዛቲ ይእቲ ዜና እንተ ሰማዕናሃ ትካት እምኔሁ
ወንዜንወክሙ ከመ እግዚአብሔር ብርሃን ውእቱ ፤
ወጽልመትሰ አልቦ ኀቤሁ ወኢአሐተኒ ።
፮ ወእመሰ ንቤለክሙ ብነ ሱታፌ ምስሌሁ ወውስተ
ጽልመት ነሐውር ንሔሱ ወኢንገብራ ለጽድቅ ወለ
ርትዕ ።
፯ ወእመሰ ውስተ ብርሃን ነሐውር በከመ ውእቱ ብር
ሃን ሱቱፋን ንሕነ በበይናቲነ ወደሙ ለኢየሱስ ክር
ስቶስ ያነጽሐነ እምኵሉ ኃጣውኢነ ።
፰ ወእመሰ ንብል አልብነ ኃጢአት ንጌጊ ለርእስነ ወአ
ልቦ ርትዕ ኀቤነ ።
፱ ወእመሰ ነገርነ ወአመነ ኃጢአተነ ምእመን ውእቱ
ወጻድቅ ከመ ይኅድግ ለነ ኃጣውኢነ ወያነጽሐነ
እምኵሉ አበሳነ ።
፲ ወእመሰ ንቤ ኢአበስነ ሐሳዊ ንሬስዮ ሎቱ ፤ ወቃሉኒ
ኢሀሎ ኀቤነ ።

ምዕራፍ ፪ ፤

### ክፍል ፪ ፤ በእንተ ተአምኖ ኃጣውእ ።

፩ ደቂቅየ ዘንተ እጽሕፍ ለክሙ ከመ ኢተአብሱ ወእ
መኒበ ዘአበሰ ጰራቅሊጦስ ብነ ኀበ አብ ኢየሱስ
ክርስቶስ ።
፪ ጻድቅ ውእቱ ይኅድግ ለነ ኃጣውኢነ ወአኮ በእንቲ
አነ ባሕቲቱ አላ በእንተ ዓለምኒ ።

# ፩ የዮሐንስ መልእክት ።

## መጀመርያው የዘብዴዎስ ልጅ የሐዋርያው የዮሐንስ መ ል እ ክ ት ።

ም ዕ ራ ፍ ፩ ።

### ክፍል ፩ ፡ ስለ እግዚአብሔር ቀዳማዊነት ።

በቀድምና የነበረውን የእሱን ነገር እንነግራችኋለን ፩
ሕይወትነቱን ለመረዳት በእጃችን ዳሥሠን በዓይናችን
አይተን በጆሮአችን ሰምተን የተረዳነው እርሱ ነው ።
ሕይወት ለእኛ ታውቃለችና አይተናት ምስክር ሆንን ፪
ከአብ ዘንድ ያለችውን ለኛ የታወቀችውን የዘለዓ
ለም ሕይወት እኛ እንነግራችኋለንና ። ዮሐ፡ ፩ ፬ ።
አየናት ሰማናት እናንተም ከእኛ ጋር አንድ ትሆኑ ፫
ዘንድ ለናንተም ነገርናችሁ አንድ መሆናችንም ከአ
ብና ከልጁ ከኢየሱስ ክርስቶስ ጋር ነው ።
ደስታችሁ በእኛ ፍጽምት ትሆን ዘንድ ይህን እንጽ ፬
ፍላችኋለን ። ዮሐ፡ ፲፭ ፲፩ ፤ ፲፯ · ፳፬ ።
ይህችም ቀድሞ ከሱ የሰማናት ናት፤ እግዚአብሔር ፭
ብርሃን እንደሆነ እንነግራችኋለን በእሱ ዘንድ ጨለማ
ምንም ምን የለም ። መዝ፡ ፻፬ ፪ ። ዮሐ፡ ፰ ፲፪ ።
ከእሱ ጋር አንድነት አለን ብንላችሁ ነገር ግን ወደ ፮
ጨለማ ብንሄድ እንዋሽለን እውነትንና ቀናውን ነገር
አንሠራም ። ምሳ፡ ፪ ፬ ።
እሱ ብርሃን እንደሆነ ወደ ብርሃን ብንሄድ ግን እኛ ፯
እርስ በርሳችን አንድነት አለን፡ የኢየሱስ ክርስቶስም
ደም ከኃጢአታችን ሁሉ ያነጻናል ።
ኃጢአት የለንም ብንል ራሳችንን ለመጕዳት እንስ ፰
ታለን ፤ በእኛ ዘንድ እምነት የለም ።
ኃጢአታችንን አምነን ብንናገር ኃጢአታችንን ይ ፱
ቅር ይለን ዘንድ የታመነ እውነተኛ ነው ፤ ከኃጢአ
ታችንም ሁሉ ያነጻናል ። ፩ ተሰ፡ ፭ ፳፬ ።
አልበደልንም ብንል ግን እሱን ሐሰተኛ እናደርገዋ ፲
ለን ቃሉም ከእኛ ዘንድ የለም ።

ም ዕ ራ ፍ ፪ ።

### ክፍል ፪ ፤ ኃጢአትን ስለ ማመን ።

ልጆቼ ! እንዳትበድሉ ይህን እጽፍላችኋለሁ ፤ የበደ ፩
ለም ቢኖር ጰራቅሊጦስ ከአብ ዘንድ አለን ኢየሱስ
ክርስቶስ ኃጢአታችንን ያስተሠርይልን ዘንድ ቸር
ነው ። ሮሜ ፰ ፴፬ ፤ ዕብ፡ ፯ ፳፭ ።
ስለ እኛ ብቻ አይደለም ስለ ዓለምም ነው እንጂ ። ፪
ቈላ፡ ምዕ፡ ፩ ቊ፡ ፳ ።

፫ ወበእንተዝ ነአምር ከመ አእመርናሁ ለእመ ዐቀብነ
ትእዛዞ ።
፬ ወዘሰ ይብል አአምሮ ወኢየዐቅብ ትእዛዞ ሐሳዊ
ውእቱ ወአልቦ ጽድቀ እግዚአብሔር በኀቤሁ ።
፭ ወዘሰ የዐቅብ ቃሎ አማን ፍቅረ እግዚአብሔር
ፍጹም ላዕሌሁ ፡ ወበዝንቱ ነአምር ከመ ቦቱ ሀለውነ።
፮ ወዘሰ ይብል ቦቱ ሀለውኩ መፍትው ይሑር በከመ
ሖረ ዝክቱ ።
፯ አኃዊነ አኮ ትእዛዘ ሐዲሰ ዘእጽሕፍ ለክሙ አላ
ትእዛዘ ብሊተ እንተ ብክሙ ትካት ፡ እስመ ትእዛዝ
ብሉይ ውእቱ ዝንቱ ቃል ዘሰማዕክሙ ።
፰ ወካዕበ ትእዛዘ ሐዲሰ እጽሕፍ ለክሙ ወውእቱ
እሙን ብክሙ ፡ ወአንትሙኒ ቦቱ እስመ ኀለፈት
ጽልመት ወብርሃን ዘበአማን ወድአ አስተርአየ ።
፱ ወዘሰ ይብል ውስተ ብርሃን ሀሎኩ ወይጸልእ ቢጾ
ሐሳዊ ውእቱ ወውስተ ጽልመት ሀሎ እስከ ይእዜ።
፲ ወዘሰ ያፈቅር ቢጾ ውስተ ብርሃን ይነብር ወአልቦ
ዕቅፍት በኀቤሁ ።
፲፩ ወዘሰ ይጸልእ ቢጾ ውስተ ጽልመት የሐውር ወኢ
የአምር ኀበ የሐውር እስመ ጽልመት አፆሮ አዕ
ይንቲሁ ።
፲፪ እጽሕፍ ለክሙ ደቂቅየ እስመ ተኀድገ ለክሙ ኃጢ
አትክሙ በእንተ ስሙ ።
፲፫ እጽሕፍ ለክሙ አበው እስመ አእመርክምዎ ለቀዳ
ማዊ ፡ እጽሕፍ ለክሙ ወራዙት እስመ ሞዕክምዎ
ለእኩይ ፡ ጸሐፍኩ ለክሙ ደቂቅየ እስመ አእመርክ
ምዎ ለአብ ።
፲፬ ጸሐፍኩ ለክሙ አበው እስመ አእመርክምዎ ለቀዳ
ማዊ ፡ ጸሐፍኩ ለክሙ ወራዙት እስመ ዕኑዓን አን
ትሙ ወቃለ እግዚአብሔር ይነብር ኀቤክሙ ፡ ወሞዕ
ክምዎ ለእኩይ ።
፲፭ ኢታፍቅርዎ ለዓለም ወኢዘሀሎ ውስተ ዓለም ወዘሰ
አፍቀሮ ለዓለም ኢሀሎ ፍቅረ እግዚአብሔር ላዕሌሁ።
፲፮ እስመ ኵሉ ዘሀሎ ውስተ ዓለም ፍትወቱ ለሥጋ
ወፍትወቱ ለዐይን ወሥራሑ ለመንበርት ኢኮነ ዝንቱ
እምኀበ አብ አላ እምዓለም ውእቱ ።
፲፯ ዓለሙኒ የኀልፍ ወፍትወቱኒ የኀልፍ ወዘሰ ይገብር
ፍትወቶ ለእግዚአብሔር ይነብር ለዓለም ።
፲፰ ደቂቅየ ዛቲ ሰዓት ደኃሪት ይእቲ ወበከመ ሰማዕ
ክሙ ከመ ይመጽእ ሐሳዌ መሲሕ ይእዜኒ ኮኑ ብዙ
ኃን ሐሳውያን መሲሕ ፡ ወበዝንቱ አእመርነ ከመ
ደኃሪት ሰዓት ይእቲ ፡ እስመ እምኔነ ወፅኡ አላ
ኢኮኑ እምኔነ ።

፩ የዮሐንስ መልእክት ።

ስለዚህም ትእዛዙን ብንጠብቅ እንደወደድነው ፫
እናውቃለን ።
ዐውቀዋለሁ የሚል ትእዛዙን የማይጠብቅ ግን ሐሰ ፬
ተኛ ነው ፡ በእሱም ዘንድ የእግዚአብሔር እውነት
የለም ። ምዕ፡ ፩ ፮ ፤ ፬ ፳ ።
ትእዛዙን የሚጠብቅ ግን ፍጹም የእግዚአብሔር ፍ ፭
ቅር አድሮበት ይኖራል በዚህ በእሱ አምነን ፀንተን
እንደምንኖር እናውቃለን ። ፩ ዮሐ፡ ፲፬ ፳፩ - ፳፫ ።
በሱ አምኜ ፀንቼ እኖራለሁ የሚል እሱ እንደኖረ ፮
ሊኖር ይገባዋል ። ዮሐ፡ ፲፭ ፬ - ፭ ።
ወንድሞቻችን ! አዲስ ትእዛዝ የምጽፍላችሁ አይ ፯
ደለም ቀድሞ በእናንተ ዘንድ የነበረውን ነበር ትእ
ዛዝ ነው እንጂ፡ ይህ የሰማችሁት ቃል ጥንት የነበረ
ትእዛዝ ነውና ።
ዳግመኛም አዲስ ትእዛዝ እጽፍላችኋለሁ እሱም ፰
በእናንተ ዘንድ የታመነ ነው እናንተም በእሱ እም
ናችሁ ፀንታችሁ ኑሩ ፡ ጨለማ አልፋለችና እውነተኛ
ብርሃንም በግልጥ ታይቷልና ። ሮሚ ፲፫ ፲፪ ።
በብርሃን ውስጥ አለሁ የሚል ወንድሙን የሚጠላ ፱
ሐሰተኛ ነው ፡ እስከ አሁን በጨለማ ውስጥ አለ ።
ወንድሙን የሚወድ ግን በብርሃን ይኖራል በእሱ ፲
ዘንድ መሰናክል የለም ። ምዕ፡ ፫ ፲፬ ።
ወንድሙን የሚጠላ ግን በጨለማ ይኖራል የሚሄ ፲፩
ድበትን አያውቅም ጨለማ ዐይኑን አሳውሮታልና ።
ልጆቼ ! እጽፍላችኋለሁ በስሙ ስለ አመናችሁ ኃጢ ፲፪
አታችሁ ተሠርዮላችኋልና ። ሉቃ፡ ፳፬ ፵፯ ።
አባቶች ! እጽፍላችኋለሁ ቀድመ ዓለም የነበረ እሱን ፲፫
ዐውቃችኋልና ፡ ጐልማሶች እጽፍላችኋለሁ ክፋውን
ድል ነሥታችኋልና፡ ልጆቼ ! ጻፍኩላችሁ አብን ዐው
ቃችሁታልና ።
አባቶች ! ጻፍኩላችሁ ቀድመ ዓለም የነበረውን አው ፲፬
ቃችሁታልና፡ ጐልማሶች ጻፍኩላችሁ ብርቱዎች ናች
ሁና ፡ የእግዚአብሔር ቃልም በእናንተ ዘንድ ፀንቶ
ይኖራልና ክፋውን ድል ነሥታችኋልና ። ኤፌ፡ ፮ ፲።
ዓለሙን በዓለም ያለውንም አትውደዱት ፡ ዓለሙን ፲፭
የወደደ የእግዚአብሔር ፍቅር የለውም ። ያዕ፡ ፬ ፬።
በዓለም ያለ ሁሉ የሥጋ ፈቃድ የዐይን አምሮት ፲፮
የአኗኗር ድካም ነውና፡ ይህ ከአብ የተገኘ አይደለም
ከዓለም እንጂ ።
ዓለሙ ያልፋል ምኞቱም ያልፋል እግዚአብሔር የሚ ፲፯
ወደውን የሚያደርግ ሰው ግን ለዘለዓለሙ ይኖራል።
ልጆቼ ! ይህች ሰዓት የኋለኛቱ ሰዓት ናት፡ ሐሳዌ ፲፰
መሲሕ እንደሚመጣ እንደሰማችሁ ዛሬም ብዙዎች
መሲሕን የሚያሳብሉ አሉ ፡ በዚህም ይህች ሰዓት
የኋላ ሰዓት እንደሆነች ዐወቅን ከእኛ ያልሆኑ ከእኛ
ወጥተዋልና ። ማቴ፡ ፳፬ ፭ - ፳፬ ።

፲፱ ወሰበሰ እምኔነ እሙንቱ እምነበሩ ምስሌነ፡ ወበሕቱ
ከመ ይትዐወቁ ከመ ኢኮኑ ኵሎሙ እምኔነ ።

፳ ወአንትሙሰ ቀብአት ብክሙ እምነ መንፈስ ቅዱስ
ወተአምሩ ኵሎ ።
፳፩ ኢጸሐፍኩ ለክሙ ከመ ዘኢተአምርዋ ለጽድቅ ፡
አላ ከመ ተአምርዋ እስመ ኵላ ሐሰት ኢኮነት እም
ጽድቅ ።
፳፪ ወመኑ ውእቱ ሐሳዊ ዘእንበለ ዘይክሕድ ወይብል
እስመ ኢየሱስ ኢኮነ መሲሐ ወዝንቱ ውእቱ ሐሳዌ
መሲሕ ዘይክሕድ በአብ ወበወልድ ።
፳፫ ወኵሉ ዘይክሕድ በወልድ ወበአብኒ ሀለወ ፡ ወዘሰ
የአምን በወልድ ወበአብኒ ሀለወ ።
፳፬ ወአንትሙሰ ዘሰማዕክሙ ትካት ለይንበር ኀቤክሙ
ወእመሰ ዘሰማዕክሙ ትካት ነበረ ኀቤክሙ ወአንት
ሙኒ ትንብሩ በአብ ወበወልድ ።

፳፭ ወዛቲ ይእቲ ተስፋ እንተ አሰፈወነ ሕይወተ ዘለዓለም ፡

፳፮ ወዘንተ ንጽሕፍ ለክሙ በእንተ እለ ያስሕቱክሙ ።
፳፯ ወአንትሙሰ ቀብአት ብክሙ እንተ ነሣእክሙ እም
ኀቤሁ ወትነብር ኀቤክሙ ወኢትፈቅዱ መኑሂ ይም
ሀርክሙ አላ መንፈሰ ዚአሁ ይሜህረክሙ በእንተ
ኵሉ ወእሙን ውእቱ ወኢኮነ ሐሰተ ፡ ወበከመ
ትምህርትክሙ ንበሩ ባቲ ።

፳፰ ወይእዜኒ ደቂቅየ ንበሩ ባቲ ከመ አመ አስተርአየ
ንርከብ ገጸ በዕለተ ደይን ወኢንትኀፈር እምኔሁ
አመ ይመጽእ ።
፳፱ ወእመሰ ርኢክሙ ከመ ጻድቅ ውእቱ አእምሩ ከመ
ኵሉ ዘይገብራ ለጽድቅ እምኔሁ ተወልደ ።

ምዕራፍ ፫ ፤

<u>ክፍል ፫ ፡ በእንተ አፍቅሮቱ ኪያነ ።</u>

፩ ወርአዩ ዘከመ እፎ ፍቅሩ ዘወሀበነ አብ ከመ ውሉደ
እግዚአብሔር ንኩን ወኮነኒ ፡ ወበእንተዝ ኢፈተወነ
ዓለም እስመ ሎቱኒ ኢያእመሮ ።

፪ አኀዊነ ይእዜሰ ደቂቀ እግዚአብሔር ንሕነ ወዓዲ
ኢተዐውቀ ለነ ምንተ ንከውን ፡ ነአምር ባሕቱ ከመ
እምከመ ተዐውቀ ለነ ከማሁ ንከውን እስመ ንሬእዮ
ሎቱ በከመ ውእቱ ።
፫ ወኵሉ ዘተወከለ ኪያሁ ያንጽሕ ርእሶ በከመ ውእቱ
ንጹሕ ።
፬ ወኵሉ ዘይገብራ ለኃጢአት ወለአበሳኒ ገብራ ውእቱ
እስመ ኃጢአት አበሳ ይእቲ ።



ከእኛስ ቢሆኑ ኖሮ ከኛ ጋራ በኖሩ ነበር፡ ነገር ግን ፲፱
ሁሉም ከእኛ ወገን እንዳልሆኑ ይታወቁ ዘንድ ከኛ
ወጥተዋል ። ግብ፡ ሐዋ፡ ፳ ፴፡ ፩ ቆሮ፡ ፲፩ ፲፱ ።
እናንተስ ከመንፈስ ቅዱስ ያገኛችሁት ልጅነት አላ ፳
ችሁና ሁሉንም ታውቃላችሁ ። ቍ፡ ፳፯ ።
እውነትን እንደማታውቋት አድርጌ አልጻፍኩላች ፳፩
ሁም እንደምታውቋት እንጂ፡ ሐሰት ሁሉ ከእውነት
ወገን አይደለችምና ።
ኢየሱስ መሲሕ አይደለም ብሎ ከሚክድ በቀር ፳፪
ሐሰተኛ ማነው? ሐሳዊ መሲሕ ይህ አብን ወልድን
የሚክድ ነው ።
ወልድን የሚክድ ሁሉ አብንም አያምንም፡ በወልድ ፳፫
የሚያምን ግን አብንም ያምናል ። ምዕ፡ ፬ ፲፭ ።
እናንተስ ቀድሞ የሰማችሁት ትምህርት በእናንተ ፳፬
ዘንድ ፀንቶ ይኑር ቀድሞ የሰማችሁት ትምህርት ከእ
ናንተ ዘንድ ከሰ እናንተም አብንና ወልድን በማመን
ፀንታችሁ ትኖራላችሁ ።
የዘለዓለም ድኅነት የምናገኝበት የነገረን ተስፋ ይህች ፳፭
ናት ።
ስለሚያስቷችሁ ይህን እንጽፍላችኋለን ። ፳፮
እናንተ ግን ከእሱ የተቀበላችሁት ቀብአት አላችሁ ፳፯
በእናንተ ዘንድ ፀንታ ትኖራለች ምንም ሊያስተምራ
ችሁ አትሹም፡ መንፈስ ቅዱስ ሁሉንም ነገር ያስተም
ራችኋል እንጂ፡ የታመነ ነው እንጂ ሐሰት አይደለም፡
በተማራችኋት በዚች ትምህርት ፀንታችሁ ኑሩ ።
ዮሐ፡ ፲፬ ፳፮፤ ፲፮ ፲፫ ።
አሁንም ልጆቼ! በእሷው ፀንታችሁ ኑሩ በፍርድ ቀን ፳፰
በተገለጸ ጊዜ ባለሟልነትን እናገኝ ዘንድ በሚመ
ጣበት ጊዜ ከእሱ የተነሣ እንፈር ። ምዕ፡ ፫ ፳፩ ።
እውነተኛ እንደሆነ ካወቃችሁም ጽድቅን የሚያደ ፳፱
ርግ ሁሉ ከእሱ እንደተወለደ ዕወቁ ። ምዕ፡ ፫ ፯-፲።

ምዕራፍ ፫ ።

<u>ክፍል ፫ ፡ እኛን ስለ መውደዱ ።</u>

የእግዚአብሔር ልጆች እንሆን ዘንድ አብ የሰጠን ፩
ፍቅሩ እንዴት እንደሆነ እዩ ሆነናልም፡ ስለዚህም
ዓለም አልወደደንም እሱን አልወደደውምና ። ዮሐ
፩ ፲፪ - ፲፫ ። ዮሐ ፲፯ ፫ ።
ወንድሞቻችን! ዛሬስ የእግዚአብሔር ልጆች ነን ግን ፪
ምን እንደምንሆን ገና አልታወቀልንም በታወቀልን
ጊዜ እንደዚያው እንደምንሆን እናውቃለን እንጂ ፡
እሱ እንደሆነ እናየዋለንና ። ሮሚ ፰ ፲፯ ።
እሱን ያመነ ሁሉ እሱ ንጹሕ እንደሆነ ራሱን ንጹሕ ፫
ያደርጋል ።
ጥቃቅኑን ኃጢአት የሚሠራ ደጋጉን ኃጢአት ሠራ፡ ፬
አበሳ ኃጢአት ናትና ።

፬ ወተአምሩ ከመ አስተርአየ ዝክቱ ከመ ያሰስል ለኃ
ጢአት ወኃጢአትሰ አልቦ ኀቤሁ ።
፮ ወኵሉ ዘበቱ ይነብር ኢይኤብስ እስመ ኵሉ ዘይኤ
ብስ ኢይሬእዮ ወኢየአምሮ ።
፯ ደቂቅየ ኢያስሕቱክሙ፤ ወኵሉ ዘይገብራ ለጽድቅ
ጻድቅ ውእቱ በከመ ዝክቱ ጻድቅ ውእቱ ።
፰ ወዘሰ ይገብራ ለኃጢአት እምነ ጋኔን ውእቱ እስመ
ቀዳሚሁ ሰይጣን አበሰ፡ ወበእንተ ዝንቱ አስተርአየ
ወልደ እግዚአብሔር ከመ ይስዐር ግብሮ ለጋኔን ።
፱ ወኵሉ ዘይትወለድ እምእግዚአብሔር ኢይገብራ
ለኃጢአት፡ እስመ ዘርአ ዚአሁ ወበቱ ይነብር ወኢ
ይክል አብሶ እስመ እምእግዚአብሔር ተወልደ ።

፲ ወበዝንቱ አሙራን ውእቶሙ ደቂቀ እግዚአብሔር
ወደቂቀ ጋኔን፡ ወኵሉ ዘኢይገብራ ለጽድቅ ኢኮነ
እምእግዚአብሔር ወከማሁ ዘኢያፈቅር ቢጾ ።

፲፩ እስመ ዛቲ ይእቲ ትእዛዝ እንተ ሰማዕክሙ ትካት
ከመ ንትፋቀር በበይናቲነ ።
፲፪ ወአኮ በከመ ቃየል ዘእምእኩይ ውእቱ ወቀተሎ
ለእኁሁ፡ ወበእንተ ምንት ቀተሎ፡ እስመ ምግባረ
ዚአሁ እኩይ ውእቱ ወዘእኁሁሰ ጽድቅ ውእቱ ።

፲፫ ወኢታንክሩ አኀዊነ እመሂ ዓለም ጸልአክሙ ።

፲፬ ንሕነሰ ነአምር ከመ ዐደውነ እሞት ውስተ ሕይወት
እስመ ናፈቅር ቢጸነ፡ ወዘሰ ኢያፈቅር ቢጾ ውስተ
ጽልመት ይነብር ።
፲፭ ኵሉ ዘይጸልእ ቢጾ ቀታሌ ነፍስ ውእቱ ወተአምሩ
ከመ ለቀታሊ ነፍስ አልቦ ሕይወት ዘለዓለም እንተ
ትሄሉ ላዕሌሁ ።
፲፮ ወበዝንቱ አእመርናሁ ለተፋቅሮ እስመ ውእቱ
መጠወ ነፍሶ በእንቲአነ ወንሕነኒ ይደልወነ ንመጡ
ነፍሰነ በእንተ ቢጽነ ።
፲፯ ወዘቦቱ መንበርተ ዝንቱ ዓለም ወይሬኢ ቢጾ ጽኑሰ
ወየዐፅ ምሕረቶ እምኔሁ እፎ ይነብር ፍቅረ እግዚ
አብሔር ላዕሌሁ ።
፲፰ ደቂቅየ ኢንትፋቀር በቃል ወበልሳን፡ ዘእንበለ በም
ግባር ወበጽድቅ ።
፲፱ ወበዝንቱ ነአምር ከመ እምጽድቅ ንሕነ፡ ወንሕነሰ
ቅድሜሁ ናመክሮ ለልብነ ።
፳ ወእመሰ ያርሰሐስሐነ ልብነ እምአበሳነ ያዐብዮ እግ
ዚአብሔር ለልብነ ወየአምር ኵሎ ።
፳፩ አኀዊነ እመሰ ኢቀለየነ ልብነ ገጽ ብነ ኀበ እግዚአ
ብሔር ።
፳፪ ወዘሂ ሰአልናሁ ንነሥእ እምኀቤሁ እስመ ትእዛዞ
ነዐቅብ ወንገብር ዘይኤድሞ ቅድሜሁ ።

ኃጢአትን ያጠፋት ዘንድ እሱ እንደ ተገለጸ ኃጢ ፬
አትም እንደሌለበት ታውቃላችሁ ። ኢሳ ፶፫ ፬ - ፭ ።
በሱም አምኖ የሚኖር ሁሉ አይበድልም፡ የሚበ ፮
ድል ሁሉ አያየውም አያውቀውምና ። ሮሜ ፮ ፲፬ ።
ልጆቼ! አያስቷችሁ ጽድቅን የሚሠራት ሁሉ እሱ ፯
ጻድቅ እንደሆነ ጻድቅ ነው ። ምዕ ፪ ፳፱ ።
ኃጢአትን የሚሠራት ከጋኔን ወገን ነው ጥንቱን ፰
ሰይጣን በድሏልና፡ ስለዚህም የጋኔንን ሥራ ይሽ
ረው ዘንድ የእግዚአብሔር ልጅ በሥጋ ተገለጠ ።
ከእግዚአብሔር የሚወለድ ሁሉ ኃጢአትን አይሠ ፱
ራትም የእሱ ልጅ ነውና፡ በእሱም አድሮበት ይኖራ
ልና፡ መበደልም አይችልም ከእግዚአብሔር ተወል
ዷልና ። ቍ ፱ ። ምዕ ፭ ፲፰ ።
በዚህም የእግዚአብሔር ልጆችና የጋኔን ልጆች ፲
ይታወቃሉ፡ ጽድቅን የማይሠራት ሁሉ ከእግዚአ
ብሔር የተወለደ አይደለም፡ ወንድሙንም የማይ
ወድ እንዲሁ ነው ።
ቀድሞ የሰማችኋት ትእዛዝ ይህች ናትና፡ እርስ ፲፩
በርሳችን እንድንፋቀር ። ዮሐ ፲፫ ፴፬ ።
ከክፉ ወገን እንደሆነና ወንድሙን እንደገደለው እን ፲፪
ደ ቃየል አይደለም፡ ስለ ምን ገደለው? የእሱ ሥራ
ክፉ የወንድሙ ሥራ ግን ጽድቅ ስለ ሆነ ነው ። ዘፍ
፬ ፰ ። ማቴ ፳፫ ፴፭ ። ይሁ ፩ ፲፩ ።
ወንድሞቻችን! ምንም ዓለም ቢጠላችሁ አታድንቁ ። ፲፫
ማቴ ፭ ፲፩ ። ዮሐ ፲፭ ፲፰ - ፲፱
እኛስ ከሞት ወደ ሕይወት እንደተሻገርን እናውቃ ፲፬
ለን፤ ባልንጀራችንን እንወዳለንና፡ ባልንጀራውን
የማይወድ ግን በጨለማ ይኖራል ። ዮሐ ፭ ፳፬ ።
ወንድሙን የሚጠላ ሁሉ ነፍሰ ገዳይ ነው፡ ለነፍሰ ፲፭
ገዳይ በእሱ ላይ ያለች ሕይወት እንደማትኖር ታው
ቃላችሁ ። ማቴ ፭ ፳፩ - ፳፪ ።
በዚህም ፍቅርን ዐወቅነው እሱ ራሱን ስለኛ አሳ ፲፮
ልፎ ሰጥቷልና፡ እኛም ስለባልንጀሮቻችን ራሳችንን
አሳልፈን መስጠት ይገባናል ።
የዚህ ዓለም ንብረት ያለው ወንድሙን ተቸግሮ ፲፯
አይቶ ከሱ ምጽዋትን የሚከለክለው የእግዚአ
ብሔር ፍቅር እንዴት ያድርበታል? ። ምዕ ፬ ፳ ።
ልጆቼ! በቃልና በመላስ አንፋቀር በእውነትና በም ፲፰
ግባር እንጂ ። ያዕ ፩ ፳፪ ። ፪ ፲፭ ።
ከጽድቅ ወገን እንደሆን በዚህ እናውቃለን፡ እኛስ ፲፱
አስቀድመን ልባችንን እንመርምረው ።
ከኃጢአታችን የተነሣ ልባችን ቢዘልፈን እግዚአብ ፳
ሔር ልባችንን ያከብረዋል ሁሉንም ያውቃል ።
ወንድሞቻችን! ልባችን የማይዘልፈን ከሆነ በእግዚ ፳፩
አብሔር ዘንድ መወደድ አለን። ምዕ ፪ ፰። ፬ ፲፯ ።
የለመንነውንም ከእሱ እንቀበላለን ትእዛዙን ጠብቀን ፳፪
በፊቱ ደስ የሚያሰኘውን እንሠራለንና። ማር ፲፩ ፳፬።

፳፫ ወዛቲ ይእቲ ትእዛዙ ከመ ንእመን በወልዱ ኢየ
ሱስ ክርስቶስ ወንትፋቀር በበይናቲነ በከመ ወሀበነ
ትእዛዘ ።
፳፬ ወዘሰ የዐቅብ ትእዛዞ ቦቱ ይነብር ወውእቱኒ ቦቱ፣
ወበዝንቱ ነአምር ከመ ይነብር ምስሌነ እምነ መን
ፈሱ ቅዱስ ዘወሀበነ ።

ምዕራፍ ፬ ፣

ክፍል ፱ ፣ በእንተ ሐሳውያን መምህራን ።

፩ አኃዊነ ለኵሉ መንፈስ ኢትእመንዎ አላ አመክርዎ
ለመንፈስ ለእመ እምኀበ እግዚአብሔር ይእቲ እስመ
ብዙኃን ሐሳውያን ነቢያት መጽኡ ውስተ ዓለም ፣
እለ ኢየአምርዎ ለኢየሱስ ክርስቶስ ።
፪ ወበዝንቱ ተአምርዋ ለመንፈሰ እግዚአብሔር ወለ
መንፈሰ ሐሰት ኵሉ መንፈስ እንተ ተአምን ከመ
ኢየሱስ ክርስቶስ መጽአ በሥጋ ሰብእ እምነ እግዚ
አብሔር ይእቲ ።
፫ ወኵሉ መንፈስ እንተ ኢተአምን በኢየሱስ ክርስቶስ
ከመ መጽአ በሥጋ ሰብእ ኢኮነት እምነ እግዚአብ
ሔር ፣ ወዝንቱ ውእቱ ሐሳዊ መሲሕ ዘሰማዕክሙ
ከመ ይመጽእ ፣ ወይእዜኒ ወድአ መጽአ ወውስተ
ዓለም ሀሎ ።
፬ ወአንትሙሰ እምነ እግዚአብሔር አንትሙ ደቂቅየ
ወሞዕክምዎ ለእኩይ እስመ የዐቢ ዘሀሎ ምስሌክሙ
እምነ ዘውስተ ዓለም ሀሎ ።
፭ ወእሙንቱሰ እምነ ዓለም እሙንቱ ወበእንተ ዝንቱ
ዘእምነ ዓለም ይነብቡ ወዓለምኒ ይሰምዖሙ ።
፮ ወንሕነሰ እምነ እግዚአብሔር ንሕነ ወዘየአምሮ ለእ
ግዚአብሔር ይሰምዐነ ፣ ወዘኢኮነ እምእግዚአብሔር
ኢይሰምዐነ ፣ ወበዝንቱ ነአምራ ለመንፈሰ ጽድቅ
ወለመንፈሰ ሐሰት ።
፯ አኃዊነ ለንትፋቀር በበይናቲነ እስመ ተፋቅሮ እምነ
እግዚአብሔር ውእቱ ወኵሉ ዘይትፋቀር እምነ እግዚ
አብሔር ውእቱ ተወልደ ወየአምሮ ለእግዚአብሔር ።
፰ ወዘሰ ኢያፈቅር ቢጾ ኢየአምሮ ለእግዚአብሔር
እስመ እግዚአብሔር ፍቅር ውእቱ ።
፱ ወበዝንቱ ተዐውቀ ፍቅሩ ለእግዚአብሔር ላዕሌነ
እስመ ለወልዱ ዋሕድ ፈነዎ ውስተ ዓለም ከመ
ንሕዮ በእንቲአሁ ።
፲ ወዝንቱ ውእቱ ፍቅሩ ለእግዚአብሔር ወአኮ ንሕነ
ዘአፍቀርናሁ አላ ውእቱ አፍቀረነ ወፈነዎ ለወልዱ
ይኅድግ ለነ ኃጣውኢነ ።
፲፩ አኃዊነ እመሰ ከመዝ አፍቀረነ እግዚአብሔር ንሕነኒ
ይደልወነ ንትፋቀር በበይናቲነ ።
፲፪ ለእግዚአብሔርሰ አልቦ ዘርእዮ ግሙራ ፣ ወእመሰ
ተፋቀርነ በበይናቲነ እግዚአብሔር ይነብር ምስሌነ
ወፍቅሩኒ ፍጹም ሀሎ ምስሌነ ።

ትእዛዙም ይህች ናት በልጁ በኢየሱስ ክርስቶስ ፳፫
እናምን ዘንድ ፣ ትእዛዙን እንደሰጠንም እርስ በርሳ
ችን እንድንዋደድ ነው ። ዮሐ ፮ ፳፱ ። ማር ፲፪ ፴፩ ።
ትእዛዙን የሚጠብቅ በእሱ አምኖ ፀንቶ ይኖራል ፣ ፳፬
እሱም አድሮበት ይኖራል ፣ በዚህም ከሰጠን ከመን
ፈስ ቅዱስ የተነሣ አድሮብን እንዲኖር እናውቃለን ።

ምዕራፍ ፬ ፣

ክፍል ፱ ፣ ስለ ሐሰተኞች መምህራን ።

ወንድሞቻችን ! ትምህርቲቱን ሁሉ አትመኗት ከእግ ፩
ዚአብሔር እንደሆነች ትምህርቲቱን መርምሯት
እንጂ ፣ ነቢያትን የሚያስተባብሉ በኢየሱስ ክርስቶስ
የማያምኑ ብዙዎች ወደ ዓለም መጥተዋልና ።
በዚህም ከእግዚአብሔር የሆነችውንና ሐሰተኛይቱን ፪
ትምህርት ታውቋታላችሁ ኢየሱስ ክርስቶስ በሥጋ
ሰው ሆኖ እንደመጣ የምታምን ትምህርት ከእግዚአ
ብሔር የተገኘች ናት ። ፩ ቆሮ ፲፪ ፫ ።
ኢየሱስ ክርስቶስ ሰው እንደሆነ የማታምን ትምህ ፫
ርት ሁላ ከእግዚአብሔር የተገኘች አይደለችም ፣
እንደሚመጣ የሰማችሁት ሐሳዊ መሲሕ ይህ ነው ፣
አሁን መጥቷል በዓለም ውስጥም አለ ።

ልጆቼ ! እናንተስ ከእግዚአብሔር ናችሁ ከፉውንም ፬
አሸንፋችሁታል ፣ በዓለም ውስጥ ካለው ከእናንተ
ጋራ ያለው ይበልጣልና ። ፪ ነገ ፪ ፲፩ ።
እነሱ ግን ከዓለም ናቸው ፣ ስለዚህም ከዓለም ያገኙ ፭
ትን ይናገራሉ ዓለሙም ይሰማቸዋል ። ዮሐ ፫ ፴፩ ።
እኛስ ከእግዚአብሔር ነን ፣ እግዚአብሔርን የሚያ ፮
ውቅ ይሰማናል ፣ ከእግዚአብሔር ያልሆነ ግን አይሰ
ማንም ፣ እውነተኛዪቱን ትምህርትና ሐሰተኛዪቱን
ትምህርት በዚህ እናውቃታለን ። ዮሐ ፰ ፵፯ ።
ወንድሞቻችን ! እርስ በእርሳችን እንፋቀር ፣ መፋቀር ፯
ከእግዚአብሔር የተገኘ ነውና የሚፋቀር ሁሉ ከእግዚ
አብሔር ተወልዷል እግዚአብሔርንም ያውቀዋል ።
ወንድሙን የማይወድ ግን እግዚአብሔርን አይወደ ፰
ውም ፣ እግዚአብሔር ፍቅር ነውና ።
በዚህም የእግዚአብሔር ፍቅሩ ለኛ ታወቀ ፣ ስለ ፱
ክሰልን እንድን ዘንድ እግዚአብሔር አንድ ልጁን
ወደ ዓለም ልኮታልና ። ዮሐ ፫ ፲፮ ። ቲቶ ፪ ፲፩ ።
የእግዚአብሔርም ፍቅሩ ይህ ነው እኛ የወደድነው ፲
አይደለም እሱ ወደደን እንጂ ፣ ኃጢአታችንን ይቅር
ይለን ዘንድም ልጁን ላከው ። ሮሜ ፭ ፲ ።
ወንድሞቻችን እግዚአብሔር እንዲህ ከወደደን ፲፩
እኛም እርስ በርሳችን ልንዋደድ ይገባናል ።
እግዚአብሔርንስ ከቶ ያየው የለም ፣ እርስ በርሳችን ፲፪
ከተዋደድን ግን እግዚአብሔር አብሮን ይኖራል ፣
ፍጹም ፍቅሩም አብሮን ይኖራል ። ዘፀአ ፴፫ ፳ ።

፲፫ ወበዝንቱ ነአምር ከመ ምስሌሁ ንነብር ወውእቱኒ ምስሌነ እምነ መንፈሱ ቅዱስ ዘወሀበነ ።

፲፬ ወንሕነኒ ርኢነ ወሰማዕነ ከመ አብ ፈነወ ወልዶ መድኅነ ዓለም ።

፲፭ ወኵሉ ዘየአምን ከመ ኢየሱስ ውእቱ ወልደ እግዚአብሔር ፡ እግዚአብሔር ይነብር ምስሌሁ ወውእቱኒ ምስለ እግዚአብሔር ።

፲፮ ወንሕነሰ አእመርነ ወአመነ እንተቦ ፍቅረ እግዚአብሔር ምስሌነ ፡ እግዚአብሔርሰ ፍቅር ውእቱ ወዘኒ ነበረ በተፋቅሮ ምስለ እግዚአብሔር ይነብር ወእግዚአብሔርኒ ምስሌሁ ።

፲፯ ወበዝንቱ ትትፌጸም ፍቅሩ ለእግዚአብሔር ምስሌነ ከመ ንርከብ ገጸ በዕለተ ደይን በኀቤሁ ፡ እስመ በከመ ከነ ውእቱ ከነ ንሕነኒ ውስተ ዝንቱ ዓለም ።

፲፰ ወአልቦ ፍርሀት ውስተ ተፋቅሮትነ አላ ተፋቅሮሰ ፍጽምት አፍአ ታወፅእ ለፍርሃት ፡ እስመ ፍርሃትሰ መቅሠፍት ቦቱ ወዘሰ ይፈርህ ኢኮነ ፍጹመ በተፋቅሮ።

፲፱ ወንሕነኒ ንትፋቀር በበይናቲነ ወናፍቅሮ ለእግዚአብሔር እስመ ውእቱ ቀደመ አፍቀረነ ።

፳ ወእመሰበ ዘይብል አፈቅሮ ለእግዚአብሔር ወይጸልእ ቢጾ ሐሳዊ ውእቱ ፡ እስመ ዘያፈቅሮ ለቢጹ ዘይሬኢ ለእግዚአብሔርኒ ያፈቅሮ ዘኢይሬኢ ፡ ወዘሰ ኢያፈቅር ቢጾ ዘይሬኢ እፎ እንከ ይክል አፍቅሮቶ ለእግዚአብሔር ዘኢይሬኢ ።

፳፩ ወዝንቱ ትእዛዝ እንተ ብነ እምኔሁ ከመ ናፍቅሮ ለእግዚአብሔር ወናፍቅር ቢጸነ ፡ ወኵሉ ዘያፈቅሮ ለእግዚአብሔር ያፍቅር ቢጾ ።

## ምዕራፍ ፭ ፡

## ክፍል ፩ ፡ በእንተ አፍቅሮትነ እግዚአብሔርሃ ።

፩ ኵሉ ዘየአምን ከመ ኢየሱስ ውእቱ መሲሕ እምነ እግዚአብሔር ተወልደ ወኵሉ ዘያፈቅሮ ለወላዲ ያፈቅር ዘኒ ተወልደ እምኔሁ ።

፪ ወበዝንቱ ነአምር ከመ ናፈቅሮ ለወልደ እግዚአብሔር ሶበ አፍቀርናሁ ለእግዚአብሔር ወገበርነ ትእዛዞ ።

፫ እስመ ዛቲ ይእቲ ፍቅሩ ለእግዚአብሔር ከመ ንዕቀብ ትእዛዞ ወትእዛዙኒ ኢኮነ ክቡደ ።

፬ እስመ ኵሉ ዘተወልደ እምእግዚአብሔር ይመውኦ ለዓለም ፡ ወዛቲ ይእቲ ሙዓቱ እንተ ሞኦ ለዓለም ሃይማኖትክሙ ።

፭ ወመኑ ውእቱ ዘይመውኦ ለዓለም ዘእንበለ ዘየአምን ከመ ኢየሱስ ውእቱ ወልደ እግዚአብሔር ።

፮ ወከመ ውእቱ መጽአ በማይ ፡ ወበደም ፡ ወበመንፈስ ኢየሱስ ክርስቶስ ።

፲፫ በዚህም ከሰጠን ከቅዱስ መንፈሱ የተነሣ ተዋሕዶ ነው እንደምንኖር እሱም አድሮብን እንደሚኖር እናውቃለን ።

፲፬ እኛም አብ የዓለም መድኃኒት አድርጎ ልጁን እንደላከው አይተናል ሰምተናል ።

፲፭ ኢየሱስ የእግዚአብሔር ልጅ እንደሆነ የሚያምን ሁሉ እግዚአብሔር አድሮበት ይኖራል ፡ እሱም ከእግዚአብሔር ጋር ይኖራል ። ምዕ ፫ ፳ ።

፲፮ እኛ የእግዚአብሔር ፍቅር ከእኛ ጋር እንዳለ አውቀን አምነናል ፡ እግዚአብሔር ፍቅር ነውና ፡ በፍቅር ፀንቶ የሚኖርም ከእግዚአብሔር ጋር ይኖራል ፡ እግዚአብሔርም አድሮበት ይኖራል ።

፲፯ በዚህም ከእኛ ጋር ያለችው የእግዚአብሔር ፍቅሩ ትፈጸምልናለች በፍርድ ቀን ከሱ ዘንድ ባለሟልነትን እናገኝ ዘንድ ፡ በዚህ ዓለም እሱ እንደሆነው እኛም እንዲሁ ሁነናልና ። ምዕ ፫ ፳፩ ።

፲፰ በፍቅራችን መፈራራት የለም ፍጹም ፍቅር፤ፍርሃትን ወደ ውጭ ታወጣታለችና ፡ ፍርሃትማ መቅሠፍት አለበት ፡ የሚፈራ ግን በፍቅር ፍጹም አይደለም ።

፲፱ እኛም እርስ በርሳችን እንዋደድ ፡ እግዚአብሔርንም እንውደደው ፡ እርሱ አስቀድሞ ወዶናልና ።

፳ እግዚአብሔርን እወደዋለሁ የሚል ወንድሙን ግን የሚጠላ ሐሰተኛ ነው ፡ የሚያየው ወንድሙን የሚወድ የማያየውን እግዚአብሔር ይወደዋልና ፡ የሚያየውን ወንድሙን የማይወድ ግን እንግዲህ የማያየውን እግዚአብሔር ሊወደው እንደምን ይችላል ? ።

፳፩ ከሱ የተቀበልነው ትእዛዝ ይህ ነው ፡ እግዚአብሔርን እንወደው ዘንድ ወንድማችንንም እንወድ ዘንድ እግዚአብሔርን የሚወድ ሁሉ ወንድሙን ይውደድ።

## ምዕራፍ ፭ ።

## ክፍል ፩ ፡ እግዚአብሔርን ስለ ማፍቀራችን።

፩ ኢየሱስ መሲሕ እንደሆነ የሚያምን ሁሉ ከእግዚአብሔር ተወለደ ፡ ወላጁን የሚወድ ሁሉም ከእሱ የተወለደውን ይወዳል ። ዮሐ ፩ ፲፪ - ፲፫ ።

፪ እግዚአብሔርን ከወደድነው ያዘዘውንም ረከደግን የእግዚአብሔርን ልጅ እንደምንወደው በዚህ እናውቃለን ምዕ ፫ ፲፬ ።

፫ የእግዚአብሔር ፍቅሩ ይህቺ ናትና ትእዛዙን እንድንጠብቅ ነው ፡ ትእዛዙም ከባድ አይደለም ።

፬ ከእግዚአብሔር የተወለደ ሁሉ ዓለምን ያሸንፈዋል ድል መንሣት ይህች ናት ዓለሙን ድል የነሣው ማመናችሁ ናት ። ዮሐ ፬ ፲፫ ። ዮሐ ፲፮ ፴፫ ።

፭ ኢየሱስ የእግዚአብሔር ልጅ እንደሆነ ከሚያምን በቀር ዓለምን ድል የሚነሣው ማነው ? ። ምዕ ፬ ፬ ።

፮ ኢየሱስ ክርስቶስ በውኃ ፡ በደም ፡ በመንፈስ ፡ እንደመጣ ከሚያምን በቀር ፤ ዮሐ ፲፱ ፴፬ - ፴፭ ።

፮ ወእከ በማይ ባሕቲቱ አላ በማይኒ ወበደምኒ ወበመ
ንፈስኒ ውእቱ ዘከሠ0 ይከውን ከመ መንፈስ ጽድቅ።
፯ እስመ ሠለስቱ እሙንቱ እለ ይከውኑ ስምዐ መን
ፈስ ወማይ ወደም ወሠለስቲሆሙ አሐዱ እሙንቱ።
፱ ወእመሰ ስምዐ ሰብእ ንነሥእ ስምዐ እግዚአብሔር
የዐቢ ፡ ወዛቲ ይእቲ ስምዑ ለእግዚአብሔር እንተ
ስምዐ ኮነ ላዕለ ወልዱ ።
፲ ሰየአምን በወልደ እግዚአብሔር ሀለወ ስምዐ እግዚ
አብሔር ምስሌሁ ፡ ወዘሰ ኢየአምን በወልዱ ሐሳዌ
ረሰዮ እስመ ኢየአምን በስምዕ እንተ ስምዐ ኮነ
እግዚአብሔር ላዕለ ወልዱ ።
፲፩ ወዛቲ ይእቲ ስምዑ ለእግዚአብሔር እንተ ወሀበነ
ሕይወተ ዘለዓለም ፡ ወዛቲ ይእቲ ሕይወት እንተ
በወልዱ ።
፲፪ ዘሀለወ ምስሌሁ ወልድ ቦቱ ሕይወት ፡ ወዘሰ ኢሀሎ
ምስለ ወልደ እግዚአብሔር አልቦቱ ሕይወት ።
፲፫ ወዘንተ ጸሐፍኩ ለክሙ ከመ ታእምሩ ከመ ብክሙ
ሕይወት ዘለዓለም እለ ትአምኑ በስሙ ለወልደ እግ
ዚአብሔር ።
፲፬ ወዛቲ ይእቲ እንተ ብነ ገጽ በኀበ እግዚአብሔር
እስመ ዘሰአልነ ኀቤሁ በስመ ዚአሁ ይሰምዐነ ።
፲፭ ወእመሰ ርኢነ ከመ ዘሰአልናሁ ይሰምዐነ ነአምር
እንከ ከመ ብነ ስእለት ዘሰአልነ በኀቤሁ ።
፲፮ ወእመሰበ ዘርእዮ ለካልኡ እንዘ ይኤብስ አበሳ ዘኢ
ክነ ለሞት ለይስአሎ ለእግዚአብሔር ከመ ያሕይዎ
ለዘይኤብስ አበሳ ዘኢኮነ ለሞት ፡ እስመቦ አበሳ ዘለ
ሞት ወኢኮነ በእንቲአሁ ዘእብል ከመ ይስአሉ ሎቱ።

፲፯ እስመ ኵሉ አበሳ ኃጢአት ይእቲ ፡ ወቦ ጌጋይ ዘኢ
ኮነ ለሞት ።
፲፰ ነአምር ከመ ኵሉ ዘተወልደ እምነ እግዚአብሔር
ኢይኤብስ አላ ዘተወልደ እምእግዚአብሔር የዐቅብ
ርእሶ ወእኩይኒ ኢይስሕጦ ።
፲፱ ነአምር ከመ እምእግዚአብሔር ንሕነ ወዓለምሰ ኵሉ
በእኪት ይቀውም ።
፳ ወነአምር ከመ ወልደ እግዚአብሔር መጽአ ወወሀ
በነ ልበ ከመ ናእምሮ ለእግዚአብሔር ዘበጽድቅ ፡
ወሀለውነ በአሚን በወልደ እግዚአብሔር በኢየሱስ
ክርስቶስ ውእቱ ዘበአማን እግዚአብሔር ወብነ ሕይ
ወት ዘለዓለም ።
፳፩ ብቲ ደቂቅየ ዕቀቡ ርእሰክሙ እምነ አማልክት ።

መልአት መልእክት ዮሐንስ ቀዳሚት ፡
ወስብሐት ለእግዚአብሔር አሜን ።



በውኃ ብቻም አይደለም በውኃ በደም የሙነት መን ፮
ፈስ እንደመሆኑ በሚመሰክር በመንፈስም ነው እንጂ።
ምስክር የሚሆኑ ሦስት ናቸውና ፡ መንፈስ ውኃና ፯
ደም ሦስቱም አንድ ናቸው ።
የሰውን ምስክርነት የምንቀበል ከሆነማ የእግዚአ ፱
ብሔር ምስክርነት ይበልጣል ፡ እግዚአብሔር ስልጁ
የመሰከረት ምስክርነቱ ይህች ናት ። ዮሐ ፰ ፲፯ ።
በእግዚአብሔር ልጅ የሚያምን የእግዚአብሔር ምስ ፲
ክርነት በርሱ ፀንቶ ይኖራል ፡ በልጁ የማያምን
ግን ሐሰተኛ አደረገው እግዚአብሔር ለልጁ በመሰ
ከረው ምስክርነት አላመነምና ። ሮሜ ፰ ፲፯ ።
የዘለዓለም ሕይወትን የሰጠን የእግዚአብሔር ምስክ ፲፩
ርነቱ ይህች ናት ፡ በልጁ ያገኘናት ሕይወትም
ይህች ናት ።
ወልድ አብሮት ያለው ሕይወት አለው ፡ ከእግዚአብ ፲፪
ሔር ልጅ ጋር ያልሆነ ግን ሕይወት የለውም ።
በእግዚአብሔር ልጅ ስም የምታምኑ የዘለዓለም ሕይ ፲፫
ወት እንዳላችሁ ታውቁ ዘንድ ይህን ጻፍኩላችሁ ።

ከእግዚአብሔር ዘንድ ያለችን ባለሟልነት ይህቺ ፲፬
ናት ፡ ከሱ ዘንድ በርሱ ስም የለመነውን ይሰማናል።
የለመነውን እንደሚሰማን ካወቅን እንግዲያስ ከእሱ ፲፭
ዘንድ የምንለምነው ልመና እንዳለን እናውቃለን።
ወንድሙን ለሞት የማያበቃ በደል ሲበድል ያየው ፲፮
ሰው ቢኖር ለሞት የማያበቃ በደል የበደለውን ሰው
ያድነው ዘንድ እግዚአብሔርን ይለምንለት ፡ ለሞት
የሚያበቃ በደል አለና፡ እንዲማልዱለት የምናገር ስለ
እርሱ አይደለም ።
በደል ሁሉ ኃጢአት ናትና ፡ ለሞት የማያበቃ በደ ፲፯
ልም አለ ።
ከእግዚአብሔር የተወለደ ሁሉ እንደማይበድል እና ፲፰
ውቃለን ፡ ከእግዚአብሔር የተወለደ ራሱን ይጠብ
ቃል እንጂ ክፉም አይነካውም ። ምዕ ፫ ፱ ።
እኛ ከእግዚአብሔር እንደሆን እናውቃለን ። ዓለሙ ፲፱
ሁሉ ግን በክፋት ፀንቶ ይኖራል ። ገላ ፩ ፬ ።
የእግዚአብሔር ልጅ ሰው ሆኖ እግዚአብሔርን በሃ ፳
ይማኖት እናውቀው ዘንድ ዕውቀት እንደ ሰጠን
እናውቃለን ፡ በእግዚአብሔር ልጅ በኢየሱስ ክርስ
ቶስ በማመን ፀንተናል ፡ እሱም በእውነት እግዚ
አብሔር ነው ፡ የዘለዓለም ሕይወት ነው ።
ልጆቼ! ጣዖትን ከማምለክ ራሳችሁን በእደ ጠብቁ። ፳፩

መጀመሪያይቱ የዮሐንስ መልእክት በእግዚአብሔር
አጋዥነት ተፈጸመች ።
ለእግዚአብሔር ምስጋና ይሁን ፡ አሜን ።

## መልእክተ ዮሐንስ ፪ ።

### ምዕራፍ ፩ ።

፩ እምነ ቀሲስ ለኅሪት ወለእግዝእት ወለደቂቃ ለአንተ
አነ አፈቅራ በጽድቅ ወበእንተ ዛቲ ጽድቅ አኮ አነ
በሕቲትየ ዘአፈቅራ አላ እለኒ የአምርዋ ለጽድቅ
ኵሎሙ ።
፪ ወበእንተ ዛቲ ጽድቅ እንተ ትነብር ኀቤነ ወትሄሉ
ምስሌነ፡ ወምስሌነ ይእቲ ለዓለም ።
፫ ሞገስ ወምሕረት ወሰላም እምኀበ እግዚአብሔር አብ
ወእምኀበ ኢየሱስ ክርስቶስ ወልዱ ለአብ እግዚአብ
ሔር ምስለ ጽድቅ ወተፋቅሮ የሃሉ ምስሌክሙ ።
፬ ተፈሣሕኩ ጥቀ እስመ ረከብኩ እምደቂቅኪ
እለ የሐውሩ በጽድቅ በከመ ነሣእነ ትእዛዘ
እምኀበ አብ ።
፭ ወይእዜኒ እስእለኪ ኦ እግዝእት ወአኮ ትእዛዘ ሐዲሰ
ዘእጽሕፍ ለኪ አላ ትእዛዘ ብሊተ እንተ ብነ ትካት
ከመ ንትፋቀር በበይናቲነ ።
፮ ወዛቲ ይእቲ ተፋቅሮትነ ከመ ንሑር በትእዛዙ
ለእግዚአብሔር ወዛቲ ይእቲ ትእዛዝ ከመ ንሑር
ባቲ እንተ ሰማዕክሙ ትካት ።
፯ እስመ ብዙኃን መስሕታን እለ መጽኡ ውስተ ዓለም
እለ ኢየአምኑ በኢየሱስ ክርስቶስ ከመ መጽአ
በሥጋ ወዝ ውእቱ መስሐቲ ሐሳዌ መሲሕ ።
፰ ዑቁ ርእሰክሙ ኢትሕጎሉ ዘገበርክሙ አላ ከመ
ዐስበ ፍጹመ ትንሥኡ ።
፱ ኵሉ ዘይናፍቅ ወኢይነብር በትምህርቱ ለክርስቶስ
ኢሀሎ እግዚአብሔር ምስሌሁ ወዘሰ ይነብር በትም
ህርቱ ለክርስቶስ በአብ ወበወልድ ሀሎ ።
፲ ወዘኒ ይመጽእ ኀቤክሙ ወዘንተ ትምህርተ ኢያመ
ጽአ ኢታብእዎ ቤትክሙ ወበሀሂ ጥቀ ኢትበልዎ ።
፲፩ እስመ ዘይቤሎ በሐ ይሳተፍ በምግባሩ እኩይ ።
፲፪ ወብዙኅ ብየ ዘእጽሕፍ ለክሙ ወኢፈቀድኩ በክር
ታስ ወበማየ ሕመት እጽሐፍ ለክሙ እስመ እትአ
መን ከመ እመጽእ ኀቤክሙ ወእፌ በአፍ እትናገ
ረክሙ ከመ ፍጹመ ይኩን ፍሥሓክሙ ።
፲፫ ይኤምኁኪ ደቂቀ እኅትኪ ኅሪት፡ ሞገስ ወተፋቅሮ
ምስሌክሙ አሜን ።

መልአት መልእክተ ዮሐንስ ዳግሚት ።
ወስብሐት ለእግዚአብሔር አሜን ።

## ፪ የዮሐንስ መልእክት ።

### ምዕራፍ ፩ ።

ከአገልጋዩ የመጣች መልእክት በእውነት እኔ ለምወ ፩
ዳት ለተመረጠችው ለእመቤቲቱና ለልጆቿ ትድረስ
ስለዚህችም እውነት እኔ ብቻ የምወዳት አይደለም
እውነትን የሚያውቋት ሁሉ ናቸው እንጂ ።
ከእኛ ዘንድ ስለምትኖር ከኛ ጋራም ስላለችው ወደ ፪
ፊትም ከእኛ ጋር ስለምትኖረው ስለዚች ጽድቅ።
በልሟልነት ይቅርታ አንድነት ከእግዚአብሔር አብ ፫
ከአብ ልጅ ከኢየሱስ ክርስቶስም ከእውነትና ከፍ
ቅር ጋር ይደረግላችሁ ።
ከአብ ዘንድ ትእዛዙን እንደ ተቀበልን ከልጆ ፬
ችሽ በእውነት ፀንተው የሚኖሩ አግኝቻለሁና
እጅግ ደስ አለኝ ።
እመቤት ! አሁንም አለምንሽለሁ እርስ በርሳችን እን ፭
ዋደድ ዘንድ ቀድሞ የተሰጠችንን የፊተኛይቱን
ትእዛዝ ነው እንጂ አዲስ ትእዛዝ የምጽፍልሽ
አይደለም ። ፩ ዮሐ፡ ፪ ፯ ።
ፍቅራችንም ይህች በእግዚአብሔር ትእዛዝ ፀንተን ፮
እንድንኖር መሆን ናት፡ ፀንተን እንድንኖርበትም
ቀድሞ የሰማችኋት ትእዛዝ ይህች ናት ።
በሥጋ እንደ መጣ በኢየሱስ ክርስቶስ የማያምኑ ፯
ብዙ አሳሳቾች ወደ ዓለም መጥተዋልና ሐሳዊ መሲሕ
የሚባል አሳሳች ይህ ነው ። ፩ ዮሐ፡ ፪ ፲፰፡ ፬ ፩ ፫።
ፍጹም ዋጋ እንድታገኙ የሠራችሁበትን እንዳታጡ ፰
ራሳችሁን ዕወቁ ። ገላ፡ ፬ ፲፩ ።
የሚጠራጠር በክርስቶስ ትምህርት ፀንቶ የማይኖር ፱
ሁሉ እግዚአብሔር ከርሱ ጋር የለም፡ በክርስቶስ
ትምህርት ፀንቶ የሚኖር ግን በአብና በወልድ አምኖ
ፀንቶ ይኖራል ። ፩ ዮሐ፡ ፪ ፳፪ - ፳፫ ።
ወደ እናንተ የሚመጣ ይህን ትምህርት የማያመጣ ፲
ውን ወደ ቤታችሁ አታስገቡት እንዴት ዋልክ እን
ዴት አደርክ እንኳ አትበሉት ። ፪ ተሰ፡ ፫ ፮ ።
እንዴት ዋልክ እንዴት አደርክ የሚለው በክፉ ፲፩
ሥራው ይተባበረዋልና ።
የምጽፍላችሁ ብዙ ነበረኝ በወረቀትና በጥቁር ቀለም ፲፪
ልጽፍላችሁ አልፈቀድኩም ደስታችሁ ፍጹም ይሆን
ዘንድ ወደ እናንተ እንደምመጣ ቃል በቃልም እን
ደማነጋግራችሁ እምናለሁና ።
የተመረጥሽ ሆይ ! የእኅትሽ ልጆች ሰላም ይሉሻል ፲፫
በለሟልነትና ፍቅር ከናንተ ጋር ይኑር፡ አሜን ።

ሁለተኛዪቱ የዮሐንስ መልእክት ተፈጸመች ።
ለእግዚአብሔር ምስጋና ይሁን፡ አሜን ።

# መልእክተ ዮሐንስ ፫።

ምዕራፍ ፩ ።

፩ እምነ ቀሲስ ለጋይዮስ ለእኁነ ዘአነ አፈቅሮ በጽድቅ ።

፪ ኦ እኁየ እስመ አነ በእንተ ኵሉ እጼሊ ለከ ከመ ትሡራሕ ፍኖትከ ወትሕዮ በዘይኤድማ ለነፍስከ ።

፫ ተፈሣሕኩ ጥቀ ሶበ መጽኡ አኀዊነ ወስምዐ ኮኑ ላዕለ ተፋቅሮትከ ከመ በጽድቅ ትሐውር ።
፬ እምዝቲ ትፍሥሕት እንተ ተዓቢ አልብየ ከመ እስ ማዕ እንዘ በጽድቅ የሐውሩ ደቂቅየ ።
፭ ኦ እኁየ እሙን ግብር ዘገበርከ ለአኀዊነ ።

፮ ወከመ ዝንቱ ግብር ለነኪራን እለ ይከውኑ ለከ ስምዐ ላዕለ ተፋቅሮትከ በቅድመ ቤተ ክርስቲያን ወዘንተ ግብረ ሠናየ ፈኖከ ቅድሚከ ዘይደሉ ለእግ ዚአብሔር ።
፯ እስመ በእንተ ስሙ ወፅኡ ወአልበ ዘነሥኡ እምነ አሕዛብ ።
፰ ወንሕነሰ አኀዊነ ይደልወነ ንትቀበሎሙ ለእለ ከመዝ ከመ ንኩን ሱታፌ ለጽድቅ ።
፱ ወጸሐፍኩ ዘንተ ለቤተ ክርስቲያን ወአቅደምኩ ወበሕቱ ዲዮጥራጢስ ዘይፈቅድ ይኩን ሊቀ ላዕሌ ሆሙ ኢይሰጠወነ ።
፲ ወበእንተ ዝንቱ አመ መጻእኩ አነ አዜክር ሎሙ ምግባሮ ዘይገብር እስመ ኢየአክሎ ዘይነብብ ንባበ እኩየ ላዕሌነ እስከ ኢይትቄበሎሙ ለአኀ ዊነ ወለእለኒ ይፈቅዱ ተቀብሎቶሙ ይከልእ ወያ ወፅኦሙ ኀዳ እምቤተ ክርስቲያን ።
፲፩ ኦ እኁየ ኢ.ትኩን ከመ ገባሬ እኪት አላ ከመ ገባሬ ሠናይት እስመ ገባሬ ሠናይት እምእግዚአብሔር ውእቱ ወገባሬ እኪትሰ ኢይሬእዮ ለእግዚአብሔር።
፲፪ ወበእንተ ድሜጥሮስኒ ስምዐ ኮነ ኵሉ ወለሊሃኒ ጽድቅ ስምዐ ኮነት ሎቱ ፡ ወንሕነኒ ስምዐ ኮነ ሎቱ ወተአምሩ ከመ ርትዕት ይእቲ ስምዕነ ።
፲፫ ብዙኀ ብየ ዘእጽሕፍ ለከ አላ ኢ.ፈቀድኩ በማየ ሕመት ወበቀለም እጽሐፍ ለከ ።
፲፬ አላ እትአመን በሕቱ ከመ ፍጡነ እሬእየከ ወእትና ገረከ አፈ በአፍ ።
፲፭ ሰላም ለከ ወይኤምኁከ አኀዊነ ፡ ወአምኁ ቢጸነ በበ አስማቲሆሙ ።

መልአት መልእክተ ዮሐንስ ሣልሲት ፡
ወስብሐት ለእግዚአብሔር አሜን ።

# ፫ የዮሐንስ መልእክት ።

ምዕራፍ ፩ ።

ከኔ ከቄሱ የተላከች መልእክት በውነት እኔ ለምወ ፩
ደው ለወንድማችን ለጋይዮስ ትድረስ። ፪ ዮሐ ቍ ፩።
ወንድሜ ሆይ ! መንገድህ ትቃናልህ ዘንድ ሰውነትህ ፪
ንም ደስ በሚያሰኛት ሕይወት ትኖር ዘንድ እኔ ስለ
ሁሉ እጸልይልሃለሁ ።
ወንድሞቻችን መጥተው በእውነት እንደምትሄድና ፫
ፍቅር መያዝህን በመስከሩልህ ጊዜ ፈጽሞ ደስ አለኝ።
ልጆቼ በውነት ፀንተው ይኖራሉ ሲባል እንድሰማ ፬
ከመሆን ከዚች ደስታ የምትበልጥ የለችም ።
ወንድሜ ሆይ ! ለወንድሞቻችን ያደረግኸው የታ ፭
መነ ሥራ ነው ።
እንደዚህ መልክም ሥራ እንደምታደርግና አስቀድ ፮
መህ እንደላክሀቸው በቤተ ክርስቲያን ፊት ስለ
ፍቅርህ ለሚመሰክሩልህ ለሌሎችም ለእግዚአብሔር
የሚገባውን አድርግ ፡ ቲቶ ፫ ፲፫ ።
ስሙን ለማስተማር ወጡ እንጂ ከአሕዛብ የተቀበ ፯
ሉት ነገር የለምና ። ማቴ ፲ ፰ ። ፪ ቆሮ ፱ ፲፪ - ፲፭።
ወንድሞቻችን ! እኛም የእውነት ተባበሪዎች እንሆን ፰
ዘንድ እንደነዚህ ያሉትን ልንቀበላቸው ይገባናል ።
ለቤተ ክርስቲያን አስቀድሜ ይህን ጻፍኩ ነገር ግን ፱
በነሱ ላይ አለቃ ሊሆን የሚወድ ዲዮጥራጢስ አይ
ቀበለንም ።
ስለዚህም እኔ በመጣሁ ጊዜ የሚሠራውን ሥራ አነ ፲
ግራቸዋለሁ በኛ ላይ የሚናገረው ነገር አልበቃው
ብሎ ወንድሞቻችንን አንቀበልም አስከ ማለት
ደርሶ ሊቀበሏቸው የሚወዱትንም ይከለክላልና ፡
ደግሞም ከቤተ ክርስቲያን ያወጣቸዋልና ።
ወንድሜ ሆይ ! እንደ በጎ አድራጊ እንጂ እንደ ክፉ ፲፩
አድራጊ አትሁን በጎ አድራጊ ከእግዚአብሔር ነውና
ክፉ የሚያደርግ ግን እግዚአብሔርን አያየውምና ።
ስለ ድሜጥሮስም ሁሉ ምስክር ሁኗል ፡ ጽድቅ ፲፪
ራሷም መስክራለታለች እኛም መስክረንለታል ፡ ምስ
ክርነታችንም እውነት እንደ ሆነች ታውቃላችሁ ።
የምጽፍልህ ብዙ ነበረኝ ግን በጥቁር ቀለምና በወረ ፲፫
ቀት ልጽፍልህ አልፈቀድኩም ። ፪ ዮሐ ቍ ፲፪ ።
በቶሎ እንደማይህና ቃል በቃልም እንደማነጋግርህ ፲፬
አምናለሁና ።
ሰላም ላንተ ይሁን ወንድሞቻችንም ሰላም ይሉ ፲፭
ሃል ፡ ባልንጀሮቻችንንም በየስማቸው ሰላም በል ።

ሦስተኛዪቱ የዮሐንስ መልእክት ተፈጸመች ።
ለእግዚአብሔር ምስጋና ይሁን ፡ አሜን ።

# መልእክተ ያዕቆብ ሐዋርያ

## መልእክተ ያዕቆብ ሐዋርያ ፡
## እኁሁ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ።

### ምዕራፍ ፩ ፡
### ክፍል ፩ ፡ በእንተ ተዓግሦ መከራ ።

፩ እምያዕቆብ ገብረ እግዚአብሔር ወእግዚእነ ኢየሱስ
ክርስቶስ ለዐሠርቱ ወክልኤቱ ሕዝበ ድዮስጶራ ሰላም
ለክሙ ።
፪ ኦ አኀው ኩኑ በኵሉ ፍሥሓ ሶበ መንሱት ይመጽ
አክሙ ዘዘዚአሁ ።
፫ እንዘ ተአምሩ ከመ መከራሃ ለሃይማኖትክሙ ትዕግ
ሥተ ይገብር ለክሙ ።
፬ ወትዕግሥትሰ ግብር ፍጹም ባቲ ከመ ትኩኑ ፍጹ
ማነ ወጥዑያነ እንዘ አልቦ ዘተኀጥአ ።
፭ ወእመሰቦ ዘኀጥአ ለጥበብ ለይስአል ኀበ ወሀቢ እግ
ዚአብሔር ዘይሁብ ለኵሉ በስፉሕ እንዘ ኢይትዔየር
ወኢይዘረኪ ወይትወሀብ ሎቱ ።
፮ ወይስአል እንዘ ይትአመን ወኢይናፍቅ እስመ ዘይ
ናፍቅሰ ይከውን ከመ ሞገደ ባሕር እንተ ይዘብጣ
ነፋስ ወያነውኃ ።
፯ ወኢይምሰሎ ለውእቱ ብእሲ ከመ ዘይነሥእ ምን
ተኒ እምኀበ እግዚአብሔር ።
፰ እስመ ብእሲ ዘክልኤ ልቡ ህውከ ውእቱ በኵሉ
ፍናዊሁ ።
፱ ለይትመካሕ እኁኒ ነዳይ በተልዕሎቱ ።
፲ ወባዕልሰ በተትሕቶቱ እስመ ከመ ፍሬ ሣዕር የኀልፍ ።
፲፩ ወእምከመ ሠረቀ ፀሐይ ምስለ ላህቡ ያየብሶ ለሣዕር
ወፍሬሁኒ ይወድቅ ወሥነ ራእዩኒ ይትኀጐል ፡ ከማ
ሁኬ ባዕልኒ በፍናዊሁ ይጸመሂ ።
፲፪ ወብፁዕ ብእሲ ዘይትዔገሣ ለእኪት እስመ ተመኪሮ
ይነሥእ አክሊለ ሕይወት ዘአሰፈዎሙ እግዚአብሔር
ለእለ ያፈቅርዎ ።
፲፫ ወእመቦ ዘይትሜከር ኢይበል እግዚአብሔር ያሜክ
ረኒ እስመ እግዚአብሔር ኢያሜክር ለእኪት ፡ ወው
እቱሰ ኢያሜክር ወኢመነሂ ።
፲፬ አላ አሐዱ አሐዱ ይትሜከር በፍትወተ እንቲአሁ
ወይወፅእ ኀቤሃ ወይደነግፅ ።
፲፭ ወፍትወትሰ እምከመ ፀንሰት ትወልዳ ለኃጢአት ፡
ወኃጢአትኒ እምከመ ተፈጸመት ትወልዳ ለሞት ።
፲፮ ኢያስሕቱክሙ አኀዊነ ፍቁራን ።
፲፯ ኵሉ ሀብት ሠናይ ወኵሉ ፍት ፍጹም እምላዕሉ ይእቲ
ትወርድ እምኀበ አቡሃ ለብርሃን ውእቱ ዘአልቦ ተው
ላጥ ኀቤሁ ወአልቦ ምንትኒ ዘያመስጥ እምእዴሁ ።

# የሐዋርያው ያዕቆብ መልእክት

## የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ወንድም ፡
## የሐዋርያው ያዕቆብ መልእክት።

### ም ዕ ራ ፍ ፩ ።
### ክፍል ፩ ፡ መከራ ስለ መታገሥ ።

የእግዚአብሔርና የጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ አገል ፩
ጋይ ከሚሆን ከያዕቆብ የተላከች መልእክት በስደት
ላሉ ለዐሥራ ሁለት ነገደ እምላክ ትድረስ ።
ወንድሞች ! ልዩ ልዩ መከራ በሚመጣባችሁ ጊዜ ፪
በፍጹም ደስታ ሰኑ ። ሮሜ ፭ ፫ ።
በሃይማኖታችሁ የሚመጣው ፈተና ትዕግሥትን እን ፫
ደሚያደርግላችሁ በውቃችሁ ።
ትዕግሥትስ ምንም ሳይጐድላችሁ ፍጹማን ጤነኞች ፬
ትሆኑ ዘንድ ፍጹም ግብር አላት ።
ጥበብን ያጣት ሰው ቢኖር ሳይገዳደር ሳይላገድ ለሁሉ ፭
በሰፊው የሚሰጥ ለጋሥ እግዚአብሔርን ይለምን ይሰ
ጠዋል ። ምሳ፡ ፪ ፫ - ፬ ፤ ማር፡ ፲፩ ፳፬ ።
ሳይጠራጠር እምኖ ይለምን የሚጠራጠር ግን ነፋስ ፮
እንደሚመታት እንደሚያንጓልላት የባሕር እዝዋፊ
ይሆናል ።
ለዚያ ሰው ከእግዚአብሔር ምን ምን የሚያገኝ ፯
አይምሰለው ።
ልቡ ሁለት የሆነ ሰው በመንገዱ ሁሉ ይታወከልና ። ፰
ድኻው ወንድማችን ከፍ ከፍ በማለቱ ደስ ይበለው። ፱
ባለ ጠጋውም በመዋረዱ ይዘን እንደ ሣር ፍሬ ያልፋ ፲
ልና ። ፩ ጴጥ፡ ፩ ፳፬ ።
ፀሐይ ከዋዕዩ ጋር በወጣ ጊዜ ሣሩን ያደርቀዋል ፲፩
ፍሬውም ይረግፋል ልምላሜውም ይጠፋል ፡ ባለጠ
ጋም እንዲሁ በሥራው ይጠፋል ። ኢሳ፡ ፵ ፮-፯።
መከራን ታግሦ የሚቀበላት ሰው ንኡድ ነው ፡ ተፈት ፲፪
ኖም እግዚአብሔር ለሚወዱት ያዘጋጀውን የክብር
አክሊል ይወርሳልና። ራእ፡ ዮሐ፡ ፫ ፲፱ ፤ ፪ ጢሞ ፬ ፰።
የሚፈተን ቢኖር እግዚአብሔር ይፈትነኛል አይበል ፲፫
እግዚአብሔር ለክፉ ነገር አይፈትንምና ፡ እሱስ ማን
ንም አይፈትንም ። ፩ ቆሮ፡ ፲ ፲፫ ።
አንዱም አንዱ በራሱ ምኞት ይፈተናል እንጂ ወደ ፲፬
እሷ ይወጣል ይደነግጣል ። ሮሜ ፯ ፯ - ፰ ።
ምኞትም ከተፀነሰች ኃጢአትን ትወልዳታለች ኃጢ ፲፭
አትም የተፈጸመች እንደሆነ ሞትን ትወልዳታለች ።
የተወደዳችሁ ወንድሞቻችን ! አያስቷችሁ ። ፲፮
መልካም ሀብት ሁሉ ፍጹም በረከትም ሁሉ ከላይ ፲፯
ናት ከብርሃን አባት ትሰጣለች ፡ መለወጥ የሌለበት
እሱ ከእሱም የሚያመልጥ ምንም ምን የለም ።

## መልእክተ ያዕቆብ ሐዋርያ ።

፲፰ እስመ በፈቃዱ ወለደነ በቃለ ጽድቁ ከመ ንኩን
ቀደምት ለፍጥረቱ ።
፲፱ ወይእዜኒ አኀዊነ ኩኑ ወይኩን ኵሉ ብእሲ ፍጡነ
ለሰሚዕ ወጐንዱየ ለነቢብ ፡ ወጐንዱየ ለመዓት ።
፳ እስመ መዓቱ ለብእሲ ጽድቀ እግዚአብሔር ኢያ
ገብር ።
፳፩ ወይእዜኒ ኀድግዋ ለኵላ ርስሐት ፡ ወለኵላ እኪት ፡
ወበየውሀት ተቀበልዎ ለቃል ዘተዘርአ ውስተ ልብ
ክሙ ዘይክል አድኅኖታ ለነፍስክሙ ።
፳፪ ወኩኑ ገባርያነ ለሕግ ወአኮ ለአፅምኦ ባሕቲቱ ፡
ሐልዩ እስኩ ለሊክሙ ።
፳፫ እመበ ዘያፀምኦ ለቃል ወኢይገብሮ ይመስል ከመ
ብእሲ ዘይሬኢ ፍጥረተ ገጹ በመጽሔት ።
፳፬ ወጠይቆ ርእሶ ኀለፈ ወረስዐ ዘከመ እፎ ውእቱ ።

፳፭ ወዘሰ ሐወጸ ውስተ ሕግ ፍጹም ዘያግዕዝ ወተዐገሠ
ኢኮነ ራስዐ ዘሰምዐ አላ ገባሬ ሕግ ውእቱ ፡ ብፁዕ
ዝንቱ በምግባሩ ።
፳፮ ወእመበ ዘይመስሎ ከመ ዘይትሐረም ለእግዚአብ
ሔር ወኢያለጕሞ ለልሳኑ ወአስሐቶ ለልቡ ለዘከ
ማሁ ከንቱ ሕርመቱ ።
፳፯ ወሕርመትሰ ንጽሕት እንተ እምኀበ እግዚአብሔር
አብ ፡ ዛቲ ይእቲ ከመ ትዕቀቡ እጓለ ማውታ ወዕቤ
ራተ በተፅናሶሙ ወትዕቀቡ ርእሰክሙ እምዓለም
ዘእንበለ ሕብቃቄ ።

## የሐዋርያው ያዕቆብ መልእክት ።

ለፍጥረቱ ተቀዳሚዎች እንሆን ዘንድ በፈቃዱ በእው ፲፰
ነተኛ ቃሉ ወልዶናልና ፡ ዮሐ፡ ፩ ፲፫ ፣ ፩ ጴጥ፡ ፩ ፳፫።
ወንድሞቻችን ! አሁንም ፅኑ ሰው ሁሉ ለመስማት ፲፱
የፈጠነ ለመናገርና ለቍጣ የዘገየ ይሁን። መክ፡ ፯ ፲ ።
የሰው ቍጣው የእግዚአብሔርን ሥራ አያሠ ፳
ራውምና ።
አሁንም ርኵሰትን ሁሉ ክፋትን ሁሉ ተዉዋት ነፍ ፳፩
ሳችሁን ማዳን የሚቻለውን በልባችሁ የተዘራውን
ቃል በገርነት ተቀበሉት ። ሮሜ ፲፫ ፲፪ ፣ ቈላ፡ ፫ ፰።
ሕግ ፈጻሚዎች ሁኑ ለመስማት ብቻ አይደለም እስኪ ፳፪
እናንተ ራሳችሁ አስቡት ። ማቴ፡ ፯ ፳፩ ፣ ሮሜ ፪ ፲፫።
ቃልን ሰምቶ የማይሠራው ቢኖር ፊቱን በመስታ ፳፫
ወት የሚያየውን ሰው ይመስላል ። ሉቃ ፡ ፮ ፵፱ ።
ራሱንም ተመልክቶ እሱ እንዴትም እንደሆነ ዘንግቶ ፳፬
ያለፈ ።
ነፃ የሚያወጣውን ፍጹሙን ሕግ የሚመለከትና ፳፭
የታገሠ የሰማውን የዘነጋ አይደለም ፈጻሚ ሕግ ነው
እንጂ ፡ ይህ በሥራው ፍጹም ነው ። ዮሐ፡ ፲፫ ፲፯ ።
ለእግዚአብሔር ብሎ ትሕርምት የያዘ የሚመስለው ፳፮
ሰው ቢኖር አንደበቱን ባይገታ ልቡናውንም ቢያስት
እንዲህ ያለው ጾሙ ከንቱ ነው ። መዝ፡ ፴፩ ፲፬ ።
ከእግዚአብሔር አብ የተፈቀደች ንጽሕት ጾምስ ፳፯
ይህቺ ናት እናት አባት የሌላቸውን ልጆች ባላቸው
የሞቱባቸውን ሴቶች ለችግራቸው እንድትሆኑ
ነው ያለ ርኵሰትም ራሳችሁን ከዓለም እንድትጠበቁ
መሆን ነው ። ኢሳ ፩ ፲፯ ፣ ፩ ጢሞ ፭ ፭ ።

### ምዕራፍ ፪ ፡
### ክፍል ፪ ፡ በእንተ ተዓርዮ ባዕል ወነዳይ ።

፩ አኀዊነ ኢትኩን ለገጸ ሰብእ ሃይማኖትክሙ እንተ
በእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ዘሎቱ ስብሐት ።
፪ ከመ እመ ቦአ ውስተ ማኅበርክሙ ብእሲ ዘኅልቀተ
ወርቅ ወዘአልባሰ ንጹሕ ፡ ወቦአ ነዳይ በአልባሰ ርሱሕ።
፫ ወትኔጽርዎ ለዘይለብስ ንጹሐ ወትብልዎ አንተሰ
ንበር ዝየ ውስተ ምሥናይ ፡ ወለነዳይሰ ትብልዎ
ቁም ከሐከ አንተሰ ወእመ አኮ ንበር ታሕተ መከ
የደ እገሪነ ።
፬ አኮኑ እንከ አድሎክሙ ለሊክሙ ወኮንክሙ መደ
ልዋነ ለሕሊና እኩይ ።
፭ ስምዑ አኀዊነ ፍቁራን አኮኑ እግዚአብሔር ኀረዮሙ
ለነዳያነ ዝ ዓለም ፡ ወእብዕልትሰ ከመ በሃይማኖቶሙ
ይወርስዋ ለመንግሥት እንተ አሰፈዎሙ ለእለ ያፈ
ቅርዎ ።
፮ ወአንትሙሰ አስተሐቀርክምዎሙ ለነዳያን ፡ አኮኑ

### ምዕራፍ ፪ ።
### ክፍል ፪ ፡ ስለ ባለ ጸጋና ድኻ መተካከል ።

ወንድሞቻችን ! ክብር ምስጋና ይግባውና በጌታችን ፩
በኢየሱስ ክርስቶስ ማመናችሁ ለሰው ይምሰል
አይሁን ።
መልካም ልብስ የለበሰ የወርቅ ቀለበት ያደረገ ሰው ፪
ወደ ስብሰባችሁ የገባ እንደሆነ አደፈ ልብስ የለበሰ
ድኻ ቢገባ ። ዘዳግ ፩ ፲፯ ። ግ ሐ ፮ ፪ ። ይሁ ፲፮ ።
መልካም ልብስ የለበሰውን አይታችሁ አንተማ ከዚህ ፫
ከመልካሙ ሥፍራ ተቀመጥ ትሉታላችሁ ፡ ድኻውን
ግን አንተስ ከዚያ ቁም ያለዚያም ከዚያ ከእግራችን
በታች ተቀመጥ ትሉታላችሁ ።
ራሳችሁ ማድላታችሁ አይደለምን ? ለክፉ አሳብም ፬
ዝግጁ ሁናችኋል ።
የተወደዳችሁ ወንድሞቻችን ! ስሙ እግዚአብሔር ፭
የዚህን ዓለም ድኾች የመረጣቸው አይደለምን ? ባለ
ጠጎችም እግዚአብሔር ለሚወዱት ያዘጋጀላቸው
መንግሥትን በሃይማኖት እንደሚወርሷት ተናግ
ሯል ። ዘፀአ ፡ ፳ ፮ ፣ ፩ ሳሙ ፪ ፪ ። ፩ ቆሮ ፡ ፩ ፳፮ ።
እናንተ ግን ነዳያንን አቃለላችኋቸው ፡ የሚቀሟችሁ ፮

እሙንቱ አብዕልት እለ ይትዔገሉክሙ ወይስሕቡ
ክሙ ውስተ ተስናናት ወአዕዋዳት ።
፯ ወእሙንቱ ይፀርፉ ላዕለ ስሙ ሠናይ ዘተሰምየ ላዕ
ሌክሙ ።
፰ ወእመሰ ትፌጽሙ ሕገ በከመ ይብል መጽሐፍ አፍ
ቅር ቢጸከ ከመ ነፍስከ ሠናየ ትገብሩ ።
፱ ወእመሰ ገጸ ትነሥኡ ኃጢአተ ትገብሩ ወይዛለፈ
ክሙ ሕግ ከመ ከሐዲ ።
፲ ወዘሰ ይገብሮ ለኵሉ ሕግ ወይስሕት በአሐቲ ፡ ኮነ
መአብሰ በኵሉ ።
፲፩ እስመ ዘይቤ ኢትሑር ኀበ ብእሲተ ብእሲ ይቤ
ኢትቅትል ነፍሰ ፡ ወእመሰ ኢተሐውር ኀበ ብእሲተ
ብእሲ ወበሕቱ ትቀትል ነፍሰ ኮንከ ውፁአ እምሕግ።
፲፪ ከመዝ ንግሩ ወከመዝ ግበሩ ከመ ዘበሕገ ግዕዛን
ሀለወክሙ ትትኰነኑ ።
፲፫ እስመ በደይንሰ አልቦ ምሒር ለዘኢገብረ ምሕረተ ፡
ወይትሜካሕ ባሕቱ በዕለተ ደይን ዘገብረ ምሕረተ ።
፲፬ ምንት ይበቍዕ አኃዊነ ለእመቦ ዘይብል ሃይማኖት
ብየ ወምግባረ ሠናይ አልብየ ፡ ቦኑ ትክል ሃይማ
ኖቱ አድኅኖቶ ።
፲፭ ለእመቦ እምአኃዊነ አው እምአኃቲነ እለ ዕሩቃን
እሙንቱ አው ኅጡአን ሲሳየ ዕለቶሙ ።
፲፮ ወቦ ዘይቤሎሙ እምኔክሙ ሑሩ በሰላም ስሐኑ
ወትጸግቡ ወኢወሀብሙ ዘይፈቅዱ ለተፅናስሙ ፡
ምንተ ይበቍዖሙ ።
፲፯ ከማሁ ሃይማኖትኒ እንተ አልባቲ ምግባረ ሠናይ ፡
ምውት ይእቲ ለሊሃ።
፲፰ አመቦ ዘይቤለከ አንተ ሃይማኖት ብከ ወአነ ምግባረ
ሠናይ ብየ ፡ አርእየኒኬ ሃይማኖተከ ዘእንበለ ምግባ
ሪከ ወአንሰ አርእየከ እምነ ምግባርየ ሃይማኖትየ ።
፲፱ አንተሰ ተአምን ከመ አሐዱ ውእቱ እግዚአብሔር
ሠናየ ትገብር ፡ ከማሁሰ አጋንንትኒ የአምኑ ወይ
ደነግፁ ።
፳ ትፈቅድኑ ታእምር አ ብእሲ ዓብድ ከመ ሃይማኖት
ዘእንበለ ምግባር ምውት ይእቲ ።
፳፩ አኮኑ አብርሃም አቡነ በምግባሩ ጸድቀ ሶበ አዕረገ
ለይስሐቅ ወልዱ ውስተ ምሥዋዕ ።
፳፪ ትሬኢኑ ከመ ሃይማኖት ትረድአ ለገቢር ፡ ወበምግ
ባሩ መልአት ወፍጽምተ ኮነት ሃይማኖቱ ።
፳፫ ወተፈጸመ ዘይብል መጽሐፍ አምነ አብርሃም በእግ
ዚአብሔር ወተኈለቆ ጽድቀ ወፍቁረ እግዚአብሔር
ተሰምየ ።
፳፬ ትሬኢኑ ከመ በምግባሩ ይጸድቅ ሰብእ ወአኮ በሃይ
ማኖቱ ባሕቲታ ።

ወደ ጸብ ክርክር ወደ ሸንጎ የሚጐትቷችሁ እነዚያ
ባለጸጎች አይደሉምን ?።
እነሱ በእናንተ ላይ የተጠራውን ገናና ስሙን ፯
ይነቅፋሉ ።
መጽሐፍ "ወንድምህን እንደ ራስህ ውደድ" እንደሚ ፰
ለው ሕግን የምትፈጽሙ ከሆነ መልካም ታደርጋ
ላችሁ ። ዘሌዋ፡ ፲፱ ፲፰ ። ማር ፡ ፲፪ ፴፩ ፡
ፊት አይታችሁ የምታደሉ ከሆነ ግን ኃጢአት ታደ ፱
ርጋላችሁ ሕግም እንደ ከሐዲ አድርጎ ይከራከ
ራችኋል ። ዘዳግ ፩ ፲፯ ።
ሕግን ሁሉ የሚፈጽም በአንዲት የሚሳሳት ፡ በሁሉ ፲
በደለኛ ሆነ ። ዘዳግ ፳፯ ፳፮ ። ማቴ ፡ ፭ ፲፱ ።
ወደ ጐልማሳ ሚስት አትሂድ ያለ እሱ ነፍስ አትግ ፲፩
ደል ብሏልና ወደ ጐልማሳ ሚስት ባትሄድ ነገር ግን
ነፍስ ብትገድል ፡ ከሕግ የወጣህ ሆንክ ። ዘጸ ፳ ፲፫ ።
በነፃነት ሕግ የሚፈረድባችሁ እንደ መሆናችሁ እን ፲፪
ዲህ አስተምሩ ፡ እንዲህ አድርጉ ። ምዕ፡ ፩ ፳፭ ።
በፍርድ ጊዜስ ምሕረት ላላደረገ ምሕረት የለም ፡ ግን ፲፫
ምሕረት ያደረገ ሰው በፍርድ ቀን ደስ ይለዋል ።
ወንድሞቻችን ! ሃይማኖት አለኝ በጎ ምግባር ግን ፲፬
የለኝም የሚል ሰው ቢኖር ምን ይጠቅማል ፡ በውኑ
ሃይማኖቱ ሊያድነው ትችላለችን ? ። ማቴ፡ ፯ ፳፮ ።
ከወንድሞቻችን ወይም ከእኅቶቻችን የተራቈቱ ፲፭
ወይም የዕለት ምግባቸውን ያጡ ቢኖሩ። ሉቃ፡ ፫ ፲፩።
ከናንተ ወገን በሰላም ሂዱ እሳት ሙቁ ትጠግባላ ፲፮
ችሁ ያላቸው ቢኖር ለችግራቸው የሚሹትን ባይሰ
ጣቸው ፡ ምን ይረባቸዋል ? ። ፩ ዮሐ፡ ፫ ፲፯ ።
እንዲሁም በጎ ምግባር የሌላት ሃይማኖት ፡ ራሷ ፲፯
የሞተች ናት ።
አንተ ሃይማኖት አለህ እኔ በጎ ምግባር አለኝ እስቲ ፲፰
ሃይማኖትህን ያለ ምግባር አሳየኝ እኔ ግን ከሥራዬ
የተነሣ ሃይማኖቴን አሳይሃለሁ ያለህ ሰው ቢኖር ።
አንተ እግዚአብሔር አንድ እንደሆነ ታምናለህ ፲፱
መልካም ታደርጋለህ እንዲህስ አጋንንትም ያምናሉ
ይደነግጣሉ ። ማር ፩ ፳፬ ። ሉቃ ፬ ፴፬ ።
አንተ ሰነፍ ሰው ! ሃይማኖት ያለ ምግባር የሞተች ፳
እንደሆነች ልታውቅ ትወዳለህን ? ። ገላ ፭ ፮ ።
አባታችን አብርሃም ልጁን ይስሐቅን ወደ መሠው ፳፩
ያው ባሳረገው ጊዜ በምግባሩ የከበረ አይደለምን?።
ዘፍጥ፡ ፳፪ ፱ ፲ ።
ሃይማኖት ለምግባር እንደረዳው ሃይማኖቱም ፳፪
በምግባሩ እንደ ተፈጸመች ታያለህን ? ።
መጽሐፍ አብርሃም በእግዚአብሔር አመነ ጽድቅ ፳፫
ሆኖም ተቈጠረለት ፡ የእግዚአብሔር ወዳጅ ተባለ
ያለው ተፈጸመ ። ዘፍጥ ፡ ፲፭ ፮ ። ኢሳ፡ ፵፩ ፰ ።
ሰው በሃይማኖቱ ብቻ ያይደለ በምግባሩ እንደሚከ ፳፬
ብር ታያለህን ? ።

፳፭ ወከማሁ ረአብኒ ዘማ በምግባሪሃ ጸድቀት ሰበ፡ ተቀበለቶሙ ለሰብአ ዐይን ወእንተ ካልእት ፍኖት አውፅአቶሙ ።

፳፮ በከመ ሥጋ ዘአልቦ መንፈስ ምውት ውእቱ፡ ከማሁ ሃይማኖትኒ እንተ አልባቲ ምግባረ ሠናይ ምውት ይእቲ ።

ምዕራፍ ፫፤

ክፍል ፫፤ ዘከመ ይደሉ ተዓግሦ ።

፩ ወኢይኩኑ እምውስቴትክሙ ብዙኃን መምህራን፡ አኀዊነ ተአምሩ ከመ እንተ ተዐቢ ደይነ ንነሥእ ።

፪ እስመ ብዙኀ ንስሕት ኵልነ፡ ወዘሰ ኢይስሕት በቃሉ ፍጹም ውእቱ ወይክል ወድየ ልጓም ለኵሉ ሥጋሁ ።

፫ ወናሁ ለአፍራስኒ ንወዲ ሎቶን ልጓመ ውስተ አፉሆን ከመ ኦሆ ይበላነ፡ ወንመይጦን ኵሎ ሥጋሆን ።

፬ ወናሁ ለአሕማርኒ ዘመጠነዝ አካሎን በኀይለ ነፋስ ሰበ ይትነድአ ወይትመየጣ ይመይጦን ብእሲ በሐዳፍ፡ እንዘ መጠነዝ ናእሱ ወያበውኦን ውስተ መርሰ ኀበ ፈቀደ ።

፭ ከማሁ ልሳንኒ ንስቲት አባል ይእቲ ወታመጽእ ዐቢያተ፡ ወናሁ እሳትኒ ንስቲት ጥቀ ዘመጠነዝ አመ ታውዒ ።

፮ ወልሳንኒ እሳት ይእቲ ለዓለም ዘዐመፃ፡ ወናሁ ልሳንኒ ንስቲት ተፈጥረት ውስተ ነፍስትነ ወታረምዖ ለሥጋነ ወትሎሉ ክቡተ ፍጥረተነ ወታውዒ ጥቀ እምገሃነም ።

፯ እስመ ኵሉ ፍጥረተ አራዊትኒ ወአዕዋፍኒ ወዘይትሐወስኒ ውስተ ባሕር ወእንስሳኒ ይገርር ለፍጥረተ እጓለ እመሕያው ።

፰ ወለልሳነ እጓለ እመሕያውሰ አልቦ ዘይክል አግርሮታ፡ እኪት ይእቲ ወአልባ ዐቅም ወምልእት ይእቲ ሕምዘ ዘይቀትል ።

፱ ባቲ ንባርኮ ለእግዚአብሔር አብ፡ ወባቲ ንረግሞ ለእጓለ እመሕያው ዘበአርአያ እግዚአብሔር ተፈጥረ ።

፲ እምአሐዱ አፍ ይፃእ ቡራኬ ወመርገም ኢይረትዕ ከመዝ አኀዊነ ይኩን ።

፲፩ ይትከሀሉኑ ይፃእ እምአሐዱ ዐይን ወእምውስተ አሐቲ ዐዘቅት ይንቅዕኑ ማይ መሪር ወማይ ጥዑም።

፲፪ ይክሉኑ አኀዊነ በለስ ዘይተ ፈርየ፡ ወእመ አኮ ወይነ በለሰ ፈርየ፡ ከማሁኬ ማይኒ መሪር ኢይከውን ጥዑመ፡ ወማይኒ ጥዑም ኢይከውን መሪረ ።

እንዲሁም ዘማይቱ ረአብ ጒብኝዎችን ተቀብላ በሌላ መንገድ ባወጣቻቸው ጊዜ በምግባሯ ከበረች ። ፳፭

ነፍስ የሌለው ሥጋ የሞተ እንደሆነ፤ እንዲሁም በጎ ምግባር የሌላት ሃይማኖት የሞተች ናት ። ቁ፡ ፲፯ ። ፳፮

ምዕራፍ ፫ ።

ክፍል ፫፤ መታገሥ ስለሚገባ ።

ወንድሞቻችን! ከፍተኛ ፍርድ እንደምንቀበል ታውቃላችሁና ከእናንተ መከከል ብዙዎች መምህራን አይሁኑ ። ማቴ ፳፫ ፰ ። ሉቃ ፮ ፴፯ ። ፩

ሁላችን ፈጽመን እንሰሳታለንና፤ በአነጋገሩ የማይስት ግን ፍጹም ነው፤ ሰውነቱን ሁሉ ወስኖ ገቶ መኖር ይቻለዋል ። ፩ ነገ ፰ ፵፮ ። ፩ ዮሐ ፩ ፰ ። ፪

እነሆ ፈረሶችን እንዲታዘዙን በአፋቸው ልጓም እናገባባቸዋለን መላ አካላቸውንም በልጓም ገተን እንመልሳቸዋለን ። መዝ፤ ፴፪ ፲፫ ። ፫

እነሆ አካላቸው ይህን ያህል የሆኑትን መርከቦችንም በነፋስ ኃይል በሚነዱበት ጊዜ ሰው ይህን ያህል ታናሽ በሆነ ዕንጨት ይመልሳቸዋል፤ ወደ ወደደው ወደብም ያደርሳቸዋል ። ፬

እንዲሁ መላስም ትንሽ አካል ስትሆን ታላላቅ ነገርን ታመጣለች፤ እነሆ እጅግ ትንሽ የሆነች እሳትም ይህን የሚያህል ዛፍ ታቃጥላለች ። ፭

መላስም ለዐመፀኛው ዓለም እሳት ናት፤ እነሆ ትንሺ መላስም በሰውነታችን ውስጥ ተፈጥራ ሥጋችንን ትለበልበዋለች፤ ውስጣዊ ሰውነታችንንም ትጠብሰዋለች ከገሃነም ይልቅ እጅግ ታቃጥላለች፤ ማቴ ፲፭ ፲፩። ፮

የወፉ የአውሬው ባሕርይ ሁሉ በባሕር የሚንቀሳቀሰውም እንስሳውም ሁሉ ለሰው ባሕርይ ይገዛል ። ፯

የሰውን መላስ ግን መግዛት የሚቻለው የለም፤ ክፉ ናት ዓቅም ግን የላትም፤ የሚገድል መርዝን የተመላች ናት ። መዝ፡ ፻፵ ፫ ። ፰

በእሷ እግዚአብሐር አብን እናመሰግነዋለን፡ በእሷም በአርአያ እግዚአብሔር የተፈጠረ ሰውን እንረግመዋለን ። ዘፍጥ፡ ፩ ፳፮ ። ፱

ወንድሞቻችን! ከንድ አፍ ማመስገንና መርገም ሊወጣ እንዲህ ሊሆን አይገባም ። ፲

ከንድ ምንጭ ከንድ ጉድጓድ የሚመር ውኃ የሚጣፍጥ ውኃ ሊወጣ ይችላልን? ወይስ ይወጣልን ። ፲፩

ወንድሞቻችን! በለስ ዘይትን ሊያፈራ ይችላልን? ወይስ ወይን በለስን ሊያፈራ ይችላልን? እንደዚሁም መራራ ውኃ ጣፋጭ አይሆንም፤ ጣፋጭ ውኃም መራራ አይሆንም ። ፲፪

፲፫ ወመኑ ጠቢብ እምኔክሙ ወምሁር ከመ ያርኢ ምግ
ባሮ በየውሀት ወበጥበብ እምሥነ ግዕዙ ።

፲፬ ወእመሰ ተቃንኦ መሪር ወከሕድ ብክሙ ውስተ
ልብክሙ፣ ኢትትመክሑ ወኢተሐሰውዋ ለጽድቅ ።
፲፭ ኢኮነት ዛቲ ጥበብ እንተ እምላዕሉ ትወርድ፣ አላ
እምድር እንተ እምነፍሰ አጋንንት ።
፲፮ እስመ ኀበ ሀለወ ተቃንኦ ህየ ሀለወ ሀውክ ወከሕድ
ወኵሉ እከየ ምግባር ።
፲፯ ወእንተሰ እምላዕሉ ጥበብ ቀዳሚሃ ንጽሕት ይእቲ
እንተ ታስተሰናእ ወእንተ በዐቅም አሆ በሃሊት
ወምልእት ምሕረተ ወፍሬሃ ሠናይ ዘእንበለ ኑፋቄ
አማኒት ።
፲፰ ወፍሬሃኒ ዘጽድቅ በሰላም ይዘራእ ለእለ ይገብርዋ
ለሰላም ።

ምዕራፍ ፬፤

<u>ክፍል ፬፣ በእንተ ፈቲው ዘኢይትረከብ ።</u>

፩ እምአይቴ ለክሙ ፀብእ ወቀትል አኮኑ እምዝየ እም
አፍቅሮ ዝሙት ዘይትገበር ውስተ አንጕዕክሙ ።

፪ ትፈትዉኒ ወኢትረክቡ ፣ ትትቃንኡኒ ወትትቃተ
ሉኒ ወበእንተዝ ኢትክሉ ድኂነ፣ ትትበአሱኒ ወትፃ
ብኡኒ ወኢትረክቡ ዘተኀሥሡ እስመ ኢትስእሉ ።
፫ ትስእሉኒ ወኢይሁቡክሙ እስመ ለእኪት ትስእሉ
ለዝሙትክሙ ከመ ተሀቡ ።

፬ ኦ ዘማውያን ኢተአምሩኑ ከመ ፍቁሩ ለዝ ዓለም
ጸላኢሁ ውእቱ ለእግዚአብሔር፣ እስመ ዘአብደረ
ፍቅሮ ለዝ ዓለም ጸላኢሁ ለእግዚአብሔር ይከውን።

፭ ወሚመ ይመስለክሙኑ ዘሐሰተ ይብል መጽሐፍ፣
ከመ ተቃንኦ ያፈቅር መንፈስ ዘየኀድር ላዕሌክሙ ።

፮ ወበሕቱ አምላክነ እንተ ተዐቢ ሞገሰ ይሁበነ፣ ወበ
እንተ ዝንቱ ይቤ እስመ ለዕቡያን ይትሄየዮሙ እግ
ዚአብሔር፣ ወለእለሰ ያቴሕቱ ርእሶሙ ይሁቦሙ
ሞገሰ ።
፯ አሆ በልዎ ለእግዚአብሔር ወእንብየ በልዎ ለጋኔን
ወይጕይይ እምኔክሙ ።
፰ ቅረብዎ ለእግዚአብሔር ወይቀርበክሙ፣ አንጽሑ
እደዊክሙ ኃጥአን ወአንጽሑ ልበክሙ፣ እለ ትና
ፍቁ ግነዩ ።
፱ ላሕዉ ወብክዩ ወለሰሐቅክሙኒ ሚጥዎ ውስተ
ላሕ፣ ወለትፍሥሕትክሙኒ ውስተ ትካዝ አግብእዎ ።
፲ አትሕቱ ርእሰክሙ ወያሌዕለክሙ እግዚአብሔር ።



ከእናንተ ወገን ከበጎ ግብሩ የተነሣ ሥራውን በቅን ፲፫
ነትና በማስተዋል ሊገልጥ የሚችል የተፈተነ አዋቂ
ማነው? ። ኤፌ ፭ ፲፭ ። ምዕ ፪ ፲፰ ።
የሚያሰዝን መቀናናትና መከዳዳት በልባችሁ ካለ ፲፬
አትመኩ፣ እውነትንም አታሳብሏት ። ኤፌ ፬ ፴፩ ።
ይህቺ ጥበብ ከምድር ከአጋንንት ጠባይ የተገኘች ፲፭
ናት እንጂ ከላይ የወረደች አይደለችም። ም ፩ ፭-፲፯።
መቀናናት ካለ ዘንድ ከዚያ መተዋወክ መከዳዳት ፲፮
ክፉ ሥራ ሁሉ አለ ። ፩ ቆሮ ፫ ፫ ።
ከላይ የወረደችው ጥበብስ ከመጀመሪያዋ ንጽሕት ፲፯
ናት፣ የምታስማማ በኃይል እሺ በጀ የምታሰኝ ቸርነ
ትን የተመላች ናት ፍሬዋም መልካም ነው ያለ ጥር
ጥር የምትታመን ናት ። ፩ ቆሮ ፪ ፮ - ፯ ።
ሰላም የሚሆን ሥራዋም የእውነት ነው፣ ሰላምን ፲፰
ለያዙ ሰዎች በፍቅር ይዘራል ። ፩ ጴጥ ፩ ፳፪ ።

ም ዕ ራ ፍ ፬ ።

<u>ክፍል ፬፣ የማይገኘውን ስለ መመኘት ።</u>

ፀብና መጋደል ከየት የመጣላችሁ ነው? ከዚህ በሰ ፩
ውነታችሁ ውስጥ የሚሠራ ዝሙትን ከመውደድ
የተነሣ አይደለምን? ። ፩ ጴጥ ፪ ፲፩ ።
ትመኛላችሁ እንጂ አታገኙም፣ ትቀናናላችሁ ትጋደ ፪
ላላችሁ ስለዚህ መዳን አትችሉም፣ ትጣላላችሁ ትዋ
ጋላችሁ የምትሹትን አታገኙም አትለምኑምና ።
መለመኑንስ ትለምናላችሁ አይሰጧችሁም፣ ለዝ ፫
ሙታችሁ ታበረክቱ ዘንድ ክፉ ነገርን ትለምናላች
ሁና ። ኢዮብ ፳፫ ፱ ። ምሳ ፩ ፳፰ ።
እናንተ ዘማውያን! ይህንን ዓለም የሚወድ የእግዚአ ፬
ብሔር ጠላት እንደሆነ አታውቁምን? የዚህን ዓለም
ፍቅር የመረጠ ሰው የእግዚአብሔር ጠላት ይሆና
ልና ። ሉቃ ፮ ፳፮ ። ሮሜ ፰ ፯ ። ፩ ዮሐ ፪ ፲፭ ።
ወይስ በእናንተ ላይ ያደረው መንፈስ መቃናትን እን ፭
ደሚወድ መጽሐፍ በሐሰት የሚናገር ይመስላችኋ
ልን? ። ገላ ። ፭ ፲፯ ።
ነገር ግን ፈጣሪያችን የምትበልጠውን ክብር ይሰጠ ፮
ናል፣ ስለዚህም እግዚአብሔር ትዕቢተኞችን ቸል
ይላቸዋል፣ ራሳቸውን ዝቅ ለሚያደርጉት ግን ክብር
ይሰጣቸዋል አለ ። ኢዮ ፳፪ ፳፱ ። ማቴ ፳፫ ፲፪ ።
እግዚአብሔርን እሺ በጀ በሉት ፣ ጋኔንን ግን እንቢ ፯
በሉት ከእናንተ ይሸሻል ። ኤፌ ፮ ፲፪ ። ምዕ ፬ ፳፯ ።
እግዚአብሔርን ቅረቡት ይቀርባችኋል፣ ኃጥአን ፰
እጃችሁን ንጹሕ አድርጉ፣ የምትጠራጠሩም ልባ
ችሁን ንጹሕ አድርጋችሁ እመኑ ። ኢሳ ፶፭ ፮።
እዘኑ አልቅሱ ሳቃችሁን ወደ ልቅሶ፣ ደስታችሁን ፱
ወደ ኃዘን መልሱ ።
ራሳችሁን አዋርዱ እግዚአብሔር ከፍ ከፍ ያደርጋ ፲
ችኋል ። ፩ ጴጥ ፭ ፮ ።

፲፩ ወኢትትሐመዩ በበይናቲክሙ አኀዊነ እስመ ዘሐ
መዩ ለካልኡ ሐመዩ ለሕገ እግዚአብሔር ወዘይግ
እዝ ካልአ ሕገ እግዚአብሔር ገአዘ ፡ ወእመሰ ሕገ
ትግእዝ ኢኮንከ ገባሬ ሕግ አላ ኮንከ ገአዚሃ ለሕግ።

፲፪ እስመ አሐዱ ውእቱ ወሃቢሃ ለሕግ ወመኰንና ለሕግ
ዘውእቱ ይክል አማስኖቲ ወአድኅኖቲ ፡ አንተኬ ምን
ትኑ አንተ ዘትግእዝ ለካልእከ ።
፲፫ ከመ እለ ይብሉ ዮም አው ጌሠመ ነሐውር ውስተ
እንታክቲ ሀገር ወንነብር ውስቴታ ወንትጌበር ወን
ረብኅ ፡ ወኢየአምሩ ዘይከውን ጌሠመ ።
፲፬ ምንትኑመ ሕይወትክሙ አኮኑ ከመ ጢስ አንትሙ
ዘለምዕር ያስተርኢ ወእምድኅሬሁ ይማስን ።

፲፭ ዘእምትቤሉ እመ ሠምረ እግዚአብሔር ወሐየውነ
ንገብር ዘንተ አው ዝክተ ።
፲፮ ወይእዜሰ ትትሜክሑ በምግባሪክሙ ፡ ወኵሉ ትም
ክሕት እንተ ከመዝ እኪት ይእቲ ።
፲፯ ወዘየአምር ገቢሮታ ለሠናይት ወኢይገብራ ኃጢአተ
ትከውኖ ።

ምዕራፍ ፭ ፡

ክፍል ፭ ፡ ዘከመ ኢይደሉ ዘጊበ ሃብት ።

፩ ንሁ ይእዜኒ አብዕልት ወብክዩ እንዘ ትግዕሩ ላዕለ
ሕርትምናክሙ እንተ ሀለዋ ትምጻእክሙ ።

፪ ብዕልክሙኒ ነቀዘ ፡ ወአልባሲክሙኒ ቈንቈነ ።

፫ ወርቅክሙኒ ወብሩርክሙኒ ዝሕለ ወዝሕሉኒ ስምዐ
ይከውን ላዕሌክሙ ወይበልዖ ለሥጋክሙ ከመ እሳት
በእንተ ዘገበርክሙ ለደኃሪ መዋዕል ።
፬ ናሁ ዐስቦሙ ለገባር ለእለ ሐረስዋ ለምድርክሙ
ሄድክምዎሙ ወዐመፅክምዎሙ ዐስቦሙ ፡ ወእለኒ
ሄድክምዎሙ የዐወይዉ ወገዓሮሙኒ ለዓፀድ በአ
ውስተ ዕዘኒሁ ለእግዚአብሔር ፀባኦት ወበጽሐ ግፍ
ዕክሙ ።
፭ ወፈጋዕክሙ ላዕለ ምድር ወአስተትክሙ ወተደለው
ክሙ ወአስበሕክሙ ልበክሙ ከመ ዘያሰብሕ ላሕመ
ለዕለተ ጥብሐት ።

፮ ወተዓደውክሙ ወቀተልክምዎ ለጻድቅ ዘእንበለ
ይትቃወመክሙ ወአሆ ይብለክሙ ።
፯ ተዓገሡ እንከ አኀዊነ እስከ ደኃሪት ዕለት አመ
ይመጽእ እግዚእክሙ ከመ ሐረሳዊ ዘይጸንሕ ፍሬሃ
ለምድር ክብርት እንዘ ይትዔገሣ ሠርከ ወነግሀ እስከ
ትሰዊ ወትፈሪ ሎቱ ወትትዐፀድ ።



ወንድሞቻችን ! እርስ በርሳችሁ አትተማሙ ወንድ ፲፩
ሙን የሚያማ የእግዚአብሔርን ሕግ ያማልና ፡ ባልን
ጀራውንም የሚነቅፍ የእግዚአብሔርን ሕግ ይነቅፋ
ልና ፡ ሕጉን የምትነቅፍ ከሆንክ ፈጻሚ ሕግ አይደለ
ህም ፡ ሕግ አፍራሽ ሆንክ እንጂ ። ፩ ጴጥ ፪ ፩ ።
ሕግን የሠራ የሕግ ባለቤት አንድ ነውና ማዳንም ፲፪
መግደልም የሚቻለው እሱ ነው እንግዲህ ባልንጀራ
ህን የምትነቅፈው አንተ ምንድነህ? ። ማቴ ፲ ፳፰ ።
ዛሬ ወይም ነገ ወደዚያች አገር ሂደን በርሷ እንኖራ ፲፫
ለን እንሠራለን ሥራም ሠርተን እንጠቀማለን እንደ
ሚሉ ነገ የሚሆነውን እንደማያውቁ ። ምሳ ፳፯ ፩።
ሕይወታችሁ ምንድነው? እናንተማ ላንድ ጊዜ ታይቶ ፲፬
ወድያው እንደሚጠፋ ጢስ አይደላችሁምን? ።
ሉቃ ፲፪ ፳ ።
እግዚአብሔር ቢፈቅድ ብንኖር ይህን ወይም ያንን ፲፭
እናደርጋለን በማለት ፈንታ ። ግብ ሐዋ ፲፰ ፳፩ ።
አሁን እናንተ በሥራችሁ ትመካላችሁ እንደዚህ ያለ ፲፮
ችው ትምክሕት ሁሉ ክፉ ናት ።
በጎ ሥራን እያወቀ የማይሠራት በደል ትሆንበታ ፲፯
ለች ። ሉቃ ፲፪ ፵፯ ። ዮሐ ፱ ፵፩ ።

ምዕራፍ ፭ ።

ክፍል ፭ ፡ ድልብን ማድለብ እንደማይገባ ።

አሁንም ባለጠጎች ! ኑና ትመጣባችሁ ዘንድ ባላት ፩
በጕስቍልናችሁ እየተጨነቃችሁ አልቅሱ ። ምሳ
፲፩ ፳፰ ። ሉቃ ፮ ፳፬ ።
ሀብታችሁ ነቀዘ ፡ ልብሳችሁንም ብል በላው ። ፪
ማቴ ፮ ፲፱ ።
ወርቃችሁና ብራችሁ ዛገ ፡ ዝገቱም ምስክር ይሆንባ ፫
ችኋል ለኋላ ዘመን ስለ አደረጋችሁትም ሥጋችሁን
እንደ እሳት ያቃጥለዋል ። ሮሜ ፪ ፭ ።
እነሆ ምድራችሁን ያረሱት የገበሬዎችን ዋጋቸውን ፬
ቀማችኋቸው በዋጋቸው በደላችኋቸው የቀማችኋቸ
ውም ይጮኻሉ ፡ ያጫጆችም ጩኸት ወደ አሸናፊው
እግዚአብሔር ገሮ ተሰምቷል ፡ (ግፋችሁም ደረሰ
ተፈጸመ) ዘዳግ ፳፬ ፲፬ - ፲፭ ። ኤር ፳፫ ፲፫ ።
በምድር ላይ ተድላ ደስታ አደረጋችሁ ሕጉን አቃ ፭
ለላችሁ ተቀማጠላችሁ ፡ ሰንጋን ለሚታረድበት ቀን
እንደሚያወፍር ልባችሁን አወፈራችሁ ። ሉቃ
፲፮ ፲፱ - ፳፭ ።
ሕጉን ተላልፋችሁ ሳይቃወማችሁ እሺ በጀ እያላ ፮
ችሁ ጻድቁን ገደላችሁት ።
እንግዲህ ወንድሞቻችን ! እስኪታሽት እስከ ታፈራ ፯
እስክትታጨድ ድረስ ጠዋትም ማታም ታግሦ የከ
በረችውን የምድር ፍሬ እንደሚጠብቅ ገበሬ ፡ ጌታ
ችሁ እስከሚመጣበት እስከ ኋለኛይቱ ቀን ታገሡ ።
ዘዳግ ፲፩ ፲፬ ። ሉቃ ፳፩ ፲፱ ። ዕብ ፲ ፴፯ ።

፰ ተዓገሡኬ አንትሙ ወአጽንዑ ልበክሙ፡ እስመ ቀርበ ምጽአቱ ለእግዚእነ።

፱ ወኢትግዐሩ አኀዊነ ላዕለ ቢጽክሙ ከመ ኢትትኰነኑ እስመ ናሁ መኰንን ኅበ መድረክ ኆኅትክሙ ይቀውም ወይጸንሕ።

፲ አርአያሃ አኀዊነ ለትዕግሥተ ተዕናስክሙ ብክሙ ነቢያት እለ ተናገሩ በቃሉ ለእግዚአብሔር ናሁ ናስተበፅዖሙ ለእለ ተዓገሡ።

፲፩ ወሰማዕክሙ ትዕግሥቶ ለኢዮብ ወርኢክሙ ዘከመ ፈጸመ ሎቱ እግዚአብሔር፡ እስመ ብዙኅ ምሕረቱ ለእግዚአብሔር ወመስተሣህል ውእቱ።

፲፪ ወእምኵሉሰ ዘይቀድም አኀዊነ ኢትምሐሉ ኢ በሰማይ፡ ወኢ በምድር፡ ወኢ በካልእ መሐላ ኢትምሐሉ ግሙራ ወኢበምንትኒ፡ አላ አሐደ ይኩን ቃልክሙ፡ እመኒ እወ እወ፡ ወእመኒ አልቦ አልቦ፡ ከመ ኢትትኰነኑ ወኢትበኡ ውስተ ደይን።

፲፫ እመቦ ዘይቴክዝ ለይጸሊ፡ ወእመቦ ዘተፈሥሐ ለይዘምር።

፲፬ ወእመቦ ዘይደዊ እምኔክሙ ለይጸውዕ ቀሳውስተ እለ ውስተ ቤተ ክርስቲያን ወይጸልዩ ላዕሌሁ ወይቀብእዎ ቀብአ ጸሎት በስሙ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ።

፲፭ ወጸሎተ ሃይማኖት ያሐይዎ ለድዉይ ወያነሥኦ እግዚአብሔር፡ ወእመኒ በቱ ኃጢአት ይትኀደግ ሎቱ።

፲፮ ተአመኑ በበይናቲክሙ ኃጢአተክሙ ወጸልዩ ላዕለ ቢጽክሙ ከመ ትሕየዉ፡ ብዙኀ ትረድእ ጸሎቱ ለጻድቅ ትክል ወታሰልጥ።

፲፯ ኤልያስ ዘከማነ ሰብእ ውእቱ ወዘከመ ነሐምም የሐምም ወጸለየ ጸሎተ ከመ ኢይዝንም ዝናም ወኢዘንመ ውስተ ምድር ሠለስተ ዓመተ ወስድስተ አውራኀ።

፲፰ ወካዕበ ጸለየ ከመ ይዝንም፡ ወወሀበ ሰማይ ዝናሞ፡ ወምድርኒ አብቈለት ፍሬሃ።

፲፱ አኀዊነ እመቦ ዘስሕተ እምኔክሙ እምጽድቅ፡ ወእመቦ ዘሚጠ እምነ ጌጋዩ።

፳ ለያእምር ከመ አድኀነ ርእሰ እምነ ሞት ወከደኖን ለብዙኃት ኃጣውኢሁ።

ተፈጸመት መልእክተ ያዕቆብ ሐዋርያ፡ እኁሁ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ።
ወስብሐት ለእግዚአብሔር አሜን።

እናንተም ታግሡ ልቡናችሁን አፅኑ ጌታ የሚመ ፰
ጣበት ጊዜ ደርሷልና። ፊልጵ ፬ ፭።

ወንድሞቻችን! እንዳይፈረድባችሁ በወንድሞቻችሁ ፱
ላይ አትዘኑ፡ እነሆ ፈራጅ ከበራፋችሁ ቆሞ ይጠብቃልና። ማቴ ፳፬ ፴፫።

ወንድሞቻችን! ታግሣችሁ ለምትቀበሉት መከራ ፲
አብነት የሚሆኑዋችሁ የእግዚአብሔርን ቃል የተናገሩ አሉላችሁ እነሆ የታገሡትን እናመሰግናቸዋለን።

የኢዮብን ትዕግሥት ሰምታችኋል እግዚአብሔርም ፲፩
የፈጸመለትን አይታችኋል፡ የእግዚአብሔር ቸርነቱ ብዙ ነውና፡ ይቅር ባይም ነውና። ኢዮ ፩ ፳፩-፳፪።

ወንድሞቻችን! ከሁሉ የሚቀድም አትማሉ፡ በሰማ ፲፪
ይም ቢሆን፡ በምድርም ቢሆን፡ በሌላ መሐላም ቢሆን፡ በምንም በምን ከቶ አትማሉ፡ ቃላችሁ አንድ ይሁን እንጂ፡ እውነት ቢሆን እውነት ነው፡ የሌለም ቢሆን የለም፡ እንዳይፈረድባችሁ ወደ ገሃነም እንዳትገቡ። ማቴ ፭ ፴፬-፴፰።

ያዘነ ቢኖር ይጸልይ፡ ደስ ያለው ቢኖር ያመስግን። ፲፫
መዝ ፶ ፲፭። ቈላ ፫ ፲፯።

ከናንተ ወገን የታመመ ሰው ቢኖር በቤተ ክርስቲ ፲፬
ያን ያሉ ቀሳውስትን ይጥራና ይጸልዩለት፡ በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ስም የተጸለየበት ዘይትንም ይቀቡት። ማር ፮ ፲፫።

በሃይማኖት የሚጸለይ ጸሎት ድውዩን ይፈውሰዋል ፲፭
እግዚአብሔርም ያስነሣዋል ኃጢአት ቢኖርበትም ይሠረይለታል። መዝ ፴ ፫። ኢሳ ፴፫ ፳፬።

እርስ በርሳችሁ ኃጢአታችሁን ተነጋገሩ፡ ትድኑም ፲፮
ዘንድ ለወንድሞቻችሁ ጸልዩ፡ የጻድቅ ሰው ጸሎቱ ብዙ ትረዳለች ግዳጅ መፈጸምም ይቻላታል። ዘፍ ፳ ፲፯። ዘኁ ፲፩ ፪። መዝ ፻፵፭ ፲፰።

ኤልያስ እንደኛ ሰው ነው እንደምንታመም ይታመ ፲፯
ማል፡ ዝናም እንዳይዘንም ጸሎትን ጸለየ፡ ሦስት ዓመት ከስድስት ወር በምድር ላይ አልዘነመም። ፩ ነገ ፲፯ ፩። ሉቃ ፬ ፳፭።

ዳግመኛም እንዲዘንም ጸለየ ሰማይም ዝናሙን ሰጠ፡ ፲፰
ምድርም የዘሩባትን አበቀለች። ፩ ነገ ፲፰ ፵፪።

ወንድሞቻችን! ከእናንተ ወገን ከጽድቅ የተሳሳተ ፲፱
ሰው ቢኖርና ከኃጢአቱ የመለሰው ሰው ቢኖር። ገላ ፮ ፩።

ራሱን ከሞት እንደ አዳነ ብዙ ኃጢአቱንም እንደ ፳
ሸፈነ ይወቅ። ፩ ጴጥ ፬ ፰፤ መዝ ፴፪ ፩።

የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ወንድም የሐዋርያው የያዕቆብ መልእክት ደረሰች ተፈጸመች።
ለእግዚአብሔር ምስጋና ይሁን፡ አሜን።

# መልእክተ ይሁዳ ። የይሁዳ መልእክት ።

## ምዕራፍ ፩ ።

### መልእክተ ይሁዳ እኁሁ ለያዕቆብ ።

፩ እምይሁዳ ገብረ እግዚአብሔር ወኢየሱስ ክርስቶስ
እኁሁ ለያዕቆብ ለእለ ያፈቅርዎ ለእግዚአብሔር አብ
ስሙያን ወጽዉዓን በኢየሱስ ክርስቶስ ።

፪ ሰላም ለክሙ ወተፋቅሮ ወሣህል ይብዛኅ ማእከ
ሌክሙ ።

፫ አኀዊነ በኵሉ አስተፋጠንኩ ከመ እጽሐፍ ለክሙ
በእንተ ሕይወተ ኵልነ እስመ ጥቀ እጽሕፍ ለክሙ
ጽሑቀ ወአስተበቍዐክሙ ከመ ትትቀነይዋ ለእንተ
ተውህበት ለቅዱሳን ሃይማኖት ።

፬ እስመ ተደመሩ ብክሙ ሰብእ ረሲዓን እለ ጽሑፋን
ቀዲሙ ለዝንቱ ደይን እለ ያፈልስዋ ለጸጋ እግዚአ
ብሔር ውስተ ዝሙቶሙ ወይክሕድዎ ለዘውእቱ
በሕቲቱ ንጉሥ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ።

፭ ወተአምሩ ምዕረሰ ከመ ኢየሱስ አድኀኖ ሕዝበ እም
ድረ ግብጽ ወበዳግምሰ ለእለ ኢአምኑ አጥፍኦሙ ።

፮ ወለመላእክቲሁኒ እለ ኢዐቀቡ ፍጥረቶሙ ወኀደ
ግዋ ለሥርዓቶሙ ውስተ ደይን አንበሮሙ ወተዓ
ሡሩ ለዕለት ዐባይ በዘለኢሆሙ አቅነዩ ርእሰሙ ።

፯ ወከማሁ ሰዶምኒ ወገሞራ ወአህጉርኒ እለ ምስሌሆን
ወበእርአያሆን ዘመዋ ወተለዋሆን በፍትወተ ዝሙት
ሚሞሙ ውስተ ደይን ዘለዓለም ወተመጠዋ ኵነኔሆን፤

፰ ወከማሁ እሉኒ እለ በሕልሞሙ ያኄምኑ ሥጋሆሙ
ወይክሕድዎ ለእግዚእሙ ወይፀርፉ ላዕለ ስብሐቲሁ።

፱ ወሚካኤልኒ ሊቀ መላእክት አመ ይትበሀሎ ለሰይ
ጣን በእንተ ሥጋሁ ለሙሴ ኢተኀበለ ቃለ ፀርፈት
ይንብብ አላ ይቤሎ ይኂስከ እግዚአብሔር ።

፲ ወእሉሰ እለ ይፀርፉ እሙንቱ ይኤብሱ በዘኢየአ
ምሩ ወሕሊናተሰ ዘሥጋ የአምሩ ከመ እንስሳ ወበቲ
ይሜረዉ ።

፲፩ አሌ ሎሙ እስመ በፍኖተ ቃየል ሖሩ ወበዐስበ ጌጋዩ
ለበለዓም ውዕዩ ወበክሕዶ ለቆሬ ወእለ ምስሌሁ
ተኀጕሉ ።

፲፪ እሉ እሙንቱ እለ በፍቅር አፍቀሩክሙ ከመ ያስሕ

## ምዕራፍ ፩ ።

### የያዕቆብ ወንድም የይሁዳ መልእክት ።

የእግዚአብሔርና የኢየሱስ ክርስቶስ አገልጋይ ለሚ ፩
ሆን ከያዕቆብ ወንድም ከይሁዳ የተላከች መልእክት
እግዚአብሔር አብን ለሚወዱ በኢየሱስ ክርስቶስ
ስም ላመኑና በስሙ ለተጠሩ ትድረስ ። ማቴ ፲፫ ፶፭ ።
ሰላም ለእናንተ ይሁን ፍቅርና ይቅርታ ይብዛላችሁ። ፪

ወንድሞቻችን ! ስለ ሁላችን ሕይወት እጽፍላችሁ ፫
ዘንድ በሁሉ ቸኰልኩ እንድጽፍላችሁ እጅግ ግድ
ነበርና ፣ ለቅዱሳን የተሰጠችውንም ሃይማኖት እንድ
ታገለግሏት እማልዳችኋለሁ ። ፪ ጢሞ ፩ ፲፫ ።
አስቀድሞ ለዚህ ፍርድ የተጻፉ በደለኞች ተቀላቅለ ፬
ውብችኋልና እነሱም እግዚአብሔርን የማይፈሩ የእግ
ዚአብሔርን ጸጋ ወደ ዝሙታቸው የሚለውጧት
አንድ እሱ ብቻ ንጉሥ የሆነ ጌታችን ኢየሱስ ክር
ስቶስን የሚክዱ ናቸው ። ቲቶ ፩ ፲፮ ።
ኢየሱስ አስቀድሞ ሕዝቡን ከግብጽ ምድር እንደ ፭
አወጣ በኋላም ያላመኑትን እንደ አጠፋቸው ታውቃ
ላችሁ ። ዘኍል ፲፬ ፴፭ ። ፩ ቆሮ ፲ ፭ ።
በሕርያቸውን ያልጠበቁ ሥርዓታቸውን የተዉ መላ ፮
እክትንም በግዞት አኖራቸው ፣ ራሳቸውን በሰንሰ
ለት ለታላቂቱ ቀን ተቀጥረዋል ። ዮሐ ፰ ፵፬ ።
እንደዚሁም ሰዶምንና ገሞራን አብረዋቸው የነበሩ ፯
ትን እነሱን አብነት አድርገው የሰሰኑትን ፣ ዝሙታ
ቸውንም ስለ መውደድ የተከተሏቸው አገሮችንም
በዘለዓለማዊ ደይን አኖራቸው ፍርዳቸውን ተቀበሉ ።
በሕልማቸው ሥጋቸውን የሚያረክሱ ፈጣሪያቸውን ፰
የሚክዱ ጌትነቱን የሚነቅፉ እሊህም እንደነዚያ
ናቸው ።
የመላእክት አለቃ ሚካኤል እንኳ ስለ ሙሴ ሥጋ ፱
ሰይጣን በተከራከረው ጊዜ የስድብ ቃል ሊናገር
አልደፈረም ፣ እግዚአብሔር ይጣላህ አለው እንጂ ።
ዳን ፲፪ ፩ ። ዘካ ፫ ፪ ።
የሚሳደቡ እሊህ እነሱ በማያውቁት ይበድላሉ የሥ ፲
ጋን አሳቦች ግን እንደ እንስሳ ያውቃሉ ፣ ግን በእ
ሷም ይጠፋሉ ፪ ጴጥ ፪ ፲፪ ።
ወዮላቸው ! በቃየል መንገድ ሂደዋልና በበለዓም ፲፩
የዓመፅ ዋጋም ተቃጥለዋልና በቆሬና ከሱም ጋር
በጠፉ ክሕደት ፀንተዋልና ። ዘፍጥ ፬ ፰ ።
ሳይወዱ እንወዳችኋለን የሚሉ እሊህ ሊያስቷችሁ ፲፪

ቱክሙ ተበፅዖን ለኃጢአቶሙ ወየሐውሩ በፍትወተ
ልበሙ ወዘእንበለ ፍርሀት ይሬእዩ ርእሰሙ ፡ ወከመ
ደመና አሙንቱ እንተ አልበቲ ዝናም እንተ ትትሀ
ወክ እምነፋስ ወከመ ዕፀዋትኒ ይቡሳት አለ አልቦን
ፍሬ አለ ካዕበ ሞቱ ወተሠረዉ ።

፲፫ ወከመ ሞገዳተ ባሕር አሙንቱ ዕቡዳት እለ ያፈል
ሕዋ ለኀሣርሙ ፡ ወከመ ከዋክብት ጽልሙታን እለ
ለፍጻሜ ጽልመቶሙ ደይን ይጸንሖሙ ለዓለመ
ዓለም ።
፲፬ በከመ ተነበየ ሄኖክ በእንቲአሆሙ ዘውእቱ ሳብዕ
እምአዳም ፡ ወይቤ ናሁ ይመጽእ እግዚአብሔር በአ
እላፊሁ ቅዱሳን መላእክት ከመ ይግበር ኩነኔ ።

፲፭ ወይፈድዮ ለኵሉ በከመ ምግባሩ ወይዛለፎሙ ለኵ
ሎሙ ኃጥአን በእንተ ኵሉ ግብረ ኃጣውኢሆሙ
ዘአበሱ ወበእንተ ኵሉ ዘነበቡ ላዕሌሁ ዘኢይከውን
ቃለ ኃጥአን ወጽልሕዋን ።
፲፮ እሉ አሙንቱ እለ ያንጐረጕሩ እስመ ቀቡጻን ተስፋ
ሆሙ እለ የሐውሩ በፍትወተ ልበሙ ወአፉሆሙኒ
ይነብብ ትዕቢተ ወያስተብዕሉ ወያደልዉ ለገጽ ወገ
ኵሉ ዘይገብሩ ከመ ይርብሖሙ ።

፲፯ ወአንትሙሰ አኀዊነ ተዘከሩ ቃለ ዘነገሩክሙ ቀዲሙ
ሐዋርያቲሁ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወዘይቤ
ሉክሙ ።
፲፰ ከመ በደኃሪ መዋዕል ይመጽኡ መስሐቃን እለ ይሚ
ሀሩ በፍትወተ ልበሙ ወያስሕቱ በኃጣውኢሆሙ ።

፲፱ እሉ እሙንቱ እለ ይስሕቡ በሥጋሆሙ ወያስሕቱ
በፍትወተ ነፍሰሙ ወመንፈስ ቅዱስ አልበሙ ።

፳ ወአንትሙሰ አኀዊነ ሕንጹ ርእሰክሙ በሃይማኖት
ቅድስት ወበመንፈስ ቅዱስ ጸልዩ ።

፳፩ ወበፍቅሩ ለእግዚአብሔር ተዓቀቡ ወተሰፈውዋ
ለምሕረቱ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ እንተ ሕይ
ወት ዘለዓለመ ዓለም ።
፳፪ እስመበ ለዘትዛለፍዎ በእንተ ኃጢአቱ ወበ ለዘትም
ሕርዎ ።
፳፫ ወበ ለዘታድኅንዎ እምውስተ እሳት ወትበልሕዎ
ወበ ዘይድኅን ፈሪሆ ወነሲሖ ወበ እለ ጸሊአሙ ዘቀ
ዳሙ፡ሥጋሆሙ ኀደጉ በሬዘ ሞልቀተ ዝሙቶሙ ።
፳፬ ወይክል እግዚአብሔር መድኀኒነ ዐቂበተክሙ ዘእን
በለ ጌጋይ ወአቅሞተክሙ ቅድመ ስብሐቲሁ ንጹሓ
ኒክሙ በትፍሥሕት ።

ነው ፡ ኃጢአትን ለመሥራት ደፋሮች ናቸው ፡ ልቡ
ናቸው በወደደው ፀንተው ይኖራሉ ፤ ሳይፈሩ ራሳ
ቸውን ከፍ አድርገው ይመለከታሉ ከነፋስ የተነሣ
እንደምትታወክ፡ ዝናም እንደሌለበት ደመና ናቸው ፤
ፍሬም እንደሌላቸው ደርቀው ተነቃቅለው እንደቀሩ
ዕንጨቶች ናቸው ።
እንደ ባሕር አዚፊት ናቸው ፤ ውርደታቸውን የሚያ ፲፫
ነሳሱዋት ዕብዶች ናቸው ፤ ብርሃን እንደሌላቸው
ለመጨረሻ ጊዜያቸውም ለዘለዓለም የጨለማ ደይን
እንደሚቈያቸው ከዋክብት ናቸው ። ኢሳ ፶፯ ፳ ።
ሄኖክ የነሱ ነገር እንደ ተናገረ ይኸውም ከአዳም ሰበ ፲፬
ተኛ ትውልድ ነው ፡ እነሆ እግዚአብሔር ይፈርድ
ዘንድ እልፍ የሆኑ ቅዱሳን መላእክትን አስከትሎ
ይመጣል ብሎ ። ዘፍጥ ፭ ፳፩ ።
ለሁሉ እንደ ሥራው ይከፍለዋል ስለ ሠሩት ኃጢአ ፲፭
ታቸው ሁሉ ኃጢአተኞች ከዳተኞች በእሱ ላይ
የማይገባውን ነገር ስለ ተናገሩ ኃጥአንን ሁሉ
ይዘልፋቸዋል ። ማቴ ፳፭ ፴፩ ።
ተስፋቸውን ስለ ቈረጡ የሚያንጐራጕሩ ልባቸው ፲፮
በወደደው የሚኖሩ በአፋቸው ትዕቢት የሚናገሩ
ሰውን ከሰው የሚያበላልጡ ፊት አይተው የሚያደሉ
እሊህ ናቸው ፤ ይህን ሁሉ የሚያደርጉት ጥቅም ያገ
ኙን መስሏቸው ነው ።
ወንድሞቻችን ! እናንተስ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ፲፯
የሾማቸው ሐዋርያት መጀመሪያ የነገሩዋችሁንና ያስ
ተማሩአችሁን ቃል አስቡ ።
በኋላ ዘመን ልቡናቸው የወደደውን የሚያስተምሩ ፲፰
በእነሱ ኃጢአት ሌላውን የሚያስቱ አሳሳቶች እንደ
ሚመጡ ። ፩ ጢሞ ፬ ፩ ። ፪ ጴጥ ፫ ፫ ።
በኃጢአታቸው የሚስቡ ልቡናቸው በወደደው የሚ ፲፱
ያስቱ መንፈስ ቅዱስ ያላደረባቸው እሊህ ናቸው ።
፩ ቆሮ ፪ ፲፬ ።
ወንድሞቻችን ! እናንተ ግን በከበረች ሃይማኖት ራሳ ፳
ችሁን አጽኑ በመንፈስ ቅዱስ ተቃኝታችሁ ጸልዩ ።
ቈላ ፪ ፯ ። ፩ ተሰ ፭ ፲፩ ።
በእግዚአብሔር ፍቅር ተጠበቁ ፡ የዘለዓለም ድኅነት ፳፩
የሚገኝበት የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስን ቸርነት
ተስፋ አድርጓት ።
በኃጢአቱ ምክንያት የምትዘልፉት አለ ፤ የምትም ፳፪
ሩትም አለ ።
ከእሳት የምታድኑት አለ ፡ ተሰዕቶ ፈርቶ የሚድንም ፳፫
አለ ፡ የቀደመ ስሕተታቸውን ጠልተው የዝሙት
ርክሰት ልብሳቸውን የተጠሙ አሉ ። ያዕ ፭ ፲፱ - ፳ ።
መድኃኒታችን እግዚአብሔርም በደል የሌላችሁ ፳፬
አድርጎ ሊጠብቃችሁ ንጹሐን አድርጎ በደስታ በጌ
ትነቱ ፊት ሊያቆማችሁ ይችላል ። ፩ ተሰ ፭ ፳፫ ።

፳፭ በእደዊሁ ለእግዚእነ ወመድኃኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ ዘሎቱ ስብሐት ወዕበይ ወኀይል ወሥልጣን እምቅድመ ኵሉ ፍጥረተ ዓለም ይእዜኒ ወዘልፈኒ ወለኵሉ ዓለማት ዘይመጽእ አሜን ።

ዓለም ሳይፈጠር ጀምሮ ዛሬም ዘወትርም ለዘለዓለ ፳፭
ሙም ክብርና ጌትነት በሚመጣውም ዓለም ሁሉ
ኀይልና ሥልጣን ገንዘቡ በሚሆን በጌታችን በመድ
ኃኒታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ሥልጣን አሜን ።
ሮሜ ፲፮ ፳፯ ። ፩ ጢሞ ፩ ፲፯ ።

መልእት መልእክተ ይሁዳ እኁሁ ለያዕቆብ ፡
ወስብሐት ለእግዚአብሔር ለዓለመ ዓለም አሜን ።

የያዕቆብ ወንድም የይሁዳ መልእክት ተፈጸመች ።
ለእግዚአብሔር ምስጋና ይሁን ለዘለዓለሙ አሜን ።



# ራእዩ ለዮሐንስ። የዮሐንስ ራእይ።

## ራእዩ ለዮሐንስ ።

## ዘዮሐንስ ኤጲስ ቆጶስ ዘቍስጥንጥንያ መጥርጶሊስ አሙ ሀለዎ ይሰደድ ።

### ምዕራፍ ፩ ፡

፩ ራእዩ ለዮሐንስ ዘከመ ርእዮ ለኢየሱስ ክርስቶስ
ዘወሀበ እግዚአብሔር ከመ ያርእዮሙ ለአግብርቲሁ
ዘሀለዎ ይኩን ፍጡነ ወዘይከውን እምድኅረዝ ።
፪ ወፈነወ ምስለ መልአኩ ኀበ ዮሐንስ ገብሩ ዘኮነ
ስምዐ በእንተ ቃለ እግዚአብሔር ወበእንተ ስምዑ
ለኢየሱስ ክርስቶስ ወበእንተ ኵሉ ዘርእየ ።
፫ ወብፁዕ ውእቱ ዘያነብብ ወዘይሰምዕ ቃለ ተነብዮቱ
ለዝንቱ መጽሐፍ ወዘየዐቅብ ዘጽሑፍ ውስቴቱ
እስመ ቅሩብ ዘመኑ ።
፬ ዘጸሐፈ ዮሐንስ ለሰብዑ አብያተ ክርስቲያናት እለ
ውስተ እስያ ፡ ሞገሱ ለክሙ ወሰላሙ እምኀበ ዘሀሎ
ወይሄሉ ዘመጽአ ወዘይመጽእ ወእምነ ሰብዐቱ መን
ፈስ ዘቅድመ መንበሩ ለኢየሱስ ክርስቶስ ።
፭ ዘውእቱ ስምዕ መሃይምን ወውእቱ ቀደመ በኵረ
ከዊነ እምነ ምውታን ዘተንሥአ ወውእቱ መኰን
ኖሙ ለነገሥተ ምድር ፡ ውእቱ ዘአፍቀረክሙ ወሐ
ፀበክሙ እምኃጣውኢክሙ በደሙ ።
፮ ወረሰየክሙ ውስተ መንግሥተ ቅድሳት አቡሁ እግ
ዚአብሔር ዘሎቱ ስብሐት ወኀይል ለዓለመ ዓለም
አሜን ።
፯ ናሁ ይመጽእ በደመና ሰማይ ወትሬእዮ ኵላ ዐይን
ወእልክቱኒ እለ ወግእዎ ወይበክዩ በእንቲአሁ
ኵሎሙ አሕዛበ ምድር ፡ እወ ወአማን ።
፰ አነ ውእቱ አልፋ ወኦ ይቤ እግዚአብሔር ዘሀሎ
ወይሄሉ ዘመጽአ ወዘይመጽእ ዘውእቱ ይመልክ
ኵሎ ።
፱ ወአነ ዮሐንስ እኁክሙ ወሱታፌክሙ በሕማም
ክሙ ወበመንግሥትክሙ ወበትዕግሥትክሙ በእ
ንተ ትዕግሥቱ ለኢየሱስ ክርስቶስ ፡ ወእንዘ ሀሎኩ
ውስተ ደሴት እንተ ስማ ፍጥሞ በእንተ ቃለ እግዚ
አብሔር ወበእንተ ስምዐ ለኢየሱስ ።
፲ መጽአ ላዕሌየ መንፈስ በዕለተ እሑድ ወሰማዕኩ
ቃለ ዐቢየ እምድኅሬየ ከመ ቃለ ቀርን ።

## የመዳኒዩቱ የቍስጥንጥንያ ኤጲስ ቆጶስ ዮሐንስ (አፈወርቅ) ተሰዶ በነበረ ጊዜ ያገኘው ዮሐንስ ወንጌላዊ ያየው ራእይ ይህ ነው ።

### ምዕራፍ ፩ ፡

ኢየሱስ ክርስቶስን እንዳየው ፈጥኖ ይደረግ ዘንድ ፩
ያለውን ፡ ከዚያም በኋላ የሚመጣውም ለባለሟሎቹ
ይገልጥላቸው ዘንድ እግዚአብሔር የገለጠለት ።
በመልአኩ ወደ አገልጋዩ ዮሐንስ የላከው ፡ ስለ እግ ፪
ዚአብሔር ቃልና ስለ ኢየሱስ ክርስቶስ ምስክር
በየው ሁሉ ላይ ምስክር የሆነ ።
የሚያነበው ንኡድ ክቡር ነው ፡ የዚህን መጽሐፍ ፫
የትንቢትን ቃል የሚሰማ ፡ በውስጡ የተጻፈውንም
የሚጠብቅ ንኡድ ክቡር ነው ዘመኑ ቀርብ ነውና ።
በእስያ ውስጥ ለሚገኙ ለሰባቱ አብያተ ክርስቲያናት ፬
ዮሐንስ የጻፈው ይህ ነው ፡ ቀድሞ ከነበረው ፡ ከሚ
ኖረው ፡ ወደዚህ ዓለም የመጣው ፡ ወደፊትም ከሚ
መጣው በኢየሱስ ክርስቶስ በዙፋኑ ፊት ካለው
ፍጹም መንፈስ ምስጋናው ሰላሙ ለናንተ ይሁን ።
የታመነ ምስክር በኵር መሆንን ጀምሮ ቀድሞ ከሙ ፭
ታን የተነሣ ፡ የምድር ነገሥታትንም የሚገዛቸው
የወደዳችሁ ፡ ከኃጢአታችሁም በደሙ ያነፃችሁ
እሱ ነው ።
አባቱ እግዚአብሔር በሚመሰገንበት መንግሥተ ፮
ሰማይ እንድትኖሩ አደረጋችሁ ምስጋና ኃይል ለዘ
ለዓለሙ ለርሱ ይሁን አሜን ።
እነሆ በሰማይ ደመና ይመጣል ፡ ዓይን ሁሉ ያየዋል ፯
እነዚያ የወጉትም ያዩታል የምድር አሕዛብም ሁሉ
ያለቅሳሉ ፡ አዎን እውነት ነው ! ።
ቀድመ ዓለም የነበረው ፡ ዓለምን አሳልፎ የሚኖረው ፰
ወደዚህ ዓለም የመጣው ፡ ወደፊትም የሚመጣው ፡
ሁሉን የሚገዛ እግዚአብሔር አልፋ ወኦ ቀዳማዊ
ደኃራዊም እኔ ነኝ አለ ።
ስለ ኢየሱስ ክርስቶስ መታገሥ ፡ በትዕግሥታች ፱
ሁና በመከራችሁ በመንግሥታችሁም ተባባሪያችሁና
ወንድማችሁ የምሆን እኔ ዮሐንስ ስለ እግዚአብ
ሔር ቃልና ስለ ኢየሱስ ክርስቶስ መመስከር ፍጥሞ
በምትባል ደሴት ሳለሁ ።
እሁድ ቀን መንፈስ ወደኔ መጣ ፡ ከወደ ኋላዬም እንደ ፲
ነጋሪት ድምፅ ያለ ታላቅ ድምፅ ሰማሁ ።

፲፩ ወይቤለኒ ጸሐፍ እንከ ዘትሬኢ ወዘትሰምዕ ውስተ
መጽሐፍ ወፈኑ ለአብያተ ክርስቲያናት ሰብዐቱ እለ
ውስተ እስያ ፥ ዘኤፌሶን ወዘሴሚርኔስ ወዘጴርጋሞን
ወዘተያጥሮን ወዘሰርዴስ ወዘፊልድልፍልያ ወዘሎ
ዶቅያ ።
፲፪ ወተመየጥኩ እርአይ ዝኩ ቃለ ዘይትናገር ምስሌየ
ወሶበ ተመየጥኩ ናሁ እሬኢ ሰብዐ መኃትወ
ዘወርቅ ።
፲፫ ወማእከለ ሰብዐ መኃትው ይነብር ከመ ወልደ እጓለ
እመሕያው ወይለብስ ልብሰ ጸዴር ወቅኑት ውስተ
ሐቌሁ በቅናት ዘወርቅ ።
፲፬ ወፀዐዳ ርእሱ ወሥዕርቱ ከመ ፀምር ፀዐዳ ወአዕይ
ንቲሁ ከመ ነደ እሳት ።
፲፭ ወእገሪሁ ከመ ብርተ ሊባኖስ ዘአርሰንዎ በእሳት ፥
ወቃሉ ከመ ቃለ ማይ ብዙኅ ።
፲፮ ወውስተ እዴሁ ዘየማን ሰብዐቱ ከከብ ፥ ወይወጽእ
እምነ አፉሁ ሰይፍ በሊሕ ዘክልኤ አፉሁ ወገጹ
ከመ ፀሐይ ብሩህ ዘያስተርኢ በኃይሉ ።
፲፯ ወሶበ ርኢክዎ ወደቁ ውስተ እገሪሁ ወኮንኩ ከመ
በድን ፥ ወአኀዘኒ በየማኑ ወአንሥአኒ ወይቤለኒ ኢት
ፍራህ አነ ውእቱ ቀዳማዊ ወደኃራዊ ዘሕያው ።
፲፰ ወእንስ ኮንኩ ከመ በድን ወይቤለኒ ናሁ ሕያው አነ
ለዓለመ ዓለም ፥ ወኅቤየ ሀሎ መራኁተ ሞት ወሲኦል።
፲፱ ጸሐፍ እንከ ዘትሬኢ ዘሀለው ወዘሀለዎ ይኩን እም
ድኅረዝ ።
፳ ወፍካሬሆሙሰ ለሰብዐቱ ከዋክብት እለ ርኢከ
ውስተ የማኑ ወሰብዐቱ መኃትው እለ ወርቅ ዝንቱ
ሰብዐቱ ከዋክብት መላእክት እሙንቱ እለ ሰብዐቱ
አብያተ ክርስቲያናት ወእልክቱኒ ሰብዐቱ መኃትው
ሰብዑ አብያተ ክርስቲያናት እሙንቱ ።

## ምዕራፍ ፪ ።

፩ ወጸሐፍ ሎቱ ለመልአከ ቤተ ክርስቲያን ዘኤፌሶን ፥
ከመዝ ይቤለከ አኃዜ ኵሉ ዘያፀንዕ ሰብዐተ ከዋክ
ብተ በየማኑ ወዘየሐውር በማእከለ ሰብዑ መኃትው
ዘወርቅ ፥ ርኢኩ ግብረከ ወፃማከ ወትዕግሥተከ ።
፪ ወከመ ኢትክል ፀዊሮቶሙ ለእኩያን እለ ይብሉ
ርእሶሙ ሐዋርያት ወኢኮኑ ወረከብኮሙ ከመ
ሐሰዉ ።
፫ ወተዐገሥከ ወፆርከ በእንተ ስምየ ወኢተቈጣዕከ ።
፬ ወበሕቱ ብ ዘአሐይሰከ እስመ ኀደገ አፍቅሮተከ
ዘቀዲሙ ።
፭ ወተዘከር እበይነ ምንት ወደቀ ነስሕ እንከ ፥ ወእመ
አከሰ እመጽእ ወእድለቅልቃ ለማኅቶትከ እምነ



እንግዲህ የምታየውንና የምትሰማውን በዚህ መጽ ፲፩
ሐፍ ጽፈህ በእስያ በኤፌሶን በሴሜርኔስ በጴርጋሞን
በተያጥሮን በሰርዴስ በፊልድልፍልያ በሎዶቅያ
ላሉት ሰባቱ አብያተ ክርስቲያናት ላክ አለኝ ።
የሚነግረኝን ቃል እሰማ ዘንድ ወደኋላዬ ተመለስኩ ፲፪
በተመለስኩም ጊዜ ሰባት የወርቅ ፋናዎችን አየሁ ።
በሰባቱም የወርቅ ፋና መካከል እንደ ሰው ልጅ ፲፫
ተቀምጧል ፥ ጸዴር የሚባል ልብስ ለብሷል ፥ በወገ
ቡም የወርቅ መታጠቂያ ታጥቋል ።
ራሱም ነጭ ነው ፥ ፀጉሩም እንደ ነጭ ሐር ነው ፥ ዓይ ፲፬
ኖቹም እንደ እሳት ነበልባል ናቸው ።
እግሮቹም በእሳት እንዳጋሉት እንደ ደጋ ብረት ፲፭
ናቸው ፥ ቃሉም እንደ ፏፏቴ ውኃ ድምፅ ነው ።
በቀኝ እጁ ሰባት ከዋክብት ተይዘዋል ፥ ከአፉም የተ ፲፮
ሳለ ሁለት ልሳን ይወጣል ፥ ፊቱም በኃይል እንደ
ሚታይ ብሩህ ፀሐይ ነው ።
በየሁትም ጊዜ ከእግሩ በታች ወድቄ እንደ በድን ፲፯
ሆንኩ ፥ በቀኝ እጁ ይዞ አስነሣኝ ፥ ቀዳማዊ ደኃራዊ
የምሆን ሕያው እኔ ነኝ አትፍራ አለኝ ።
እኔ ግን ነፍስ እንደ ተለየው በድን ሆንኩ፡ እነሆም ለዘ ፲፰
ለዓለሙ ሕያው ነኝ ፥ የሞትና የመቃብር መክፈቻ
ከኔ ዘንድ አለ አለኝ ።
እንግዲህ የምታየውን የሆነውም ከዚህ በኋላ ይሆን ፲፱
ዘንድ ያለውንም ጻፍ አለኝ ።
በቀኝ እጁ ተይዘው ያየሃቸው የሰባቱ ከዋክብትና ፳
የሰባቱም የወርቅ ፋናዎች ትርጓሜያቸው ይህ ነው ፥
ሰባቱ ከዋክብት በሰባቱ አብያተ ክርስቲያናት የተ
ሾሙ አለቆች ናቸው ፥ እሊያም ሰባቱ ፋናዎች ሰባቱ
አብያተ ክርስቲያናት ናቸው ።

## ምዕራፍ ፪ ።

ለኤፌሶን ቤተ ክርስቲያን አለቃ ጻፍለት ፥ ሁሉን ፩
የሚገዛ ፥ ሰባቱንም ከዋክብት በቀኝ እጁ የሚያፀና ፥
በወርቅ ፋናዎች መካከል የሚኼድ እሱ እንዲህ አለህ።
ሥራሕን ድካምህን ትዕግሥትህን አየሁ ፥ ሳይሆኑ ፪
በራሳቸው ሐዋርያት ነን የሚሉት ክፉዎችንም መታ
ገሣቸው እንዳይቻልህ ዐወቅሁ ፥ ሐሰተኞች ሁነው
አግኝተሃቸዋልና ።
ስለ ስሜም መከራውን ስትሰለች ታግሠህ ተቀብ ፫
ለሃል ።
ነገር ግን የምነቅፍብህ አለኝ ፥ የቀደመ ፍቅርህን ፬
ትተሃልና ።
ስለምን እንደ ወደቅህ አስተውል እንግዲህ ተመ ፭
ለስ ፥ ያለዚያ ግን በትመለስ የቀደመ ሥራህንም

መከና እመ ኢነሳሕከ ወከመ ቀዲሙ ግብረከ እመ
ኢገበርከ ።
፮ ወዝንቱሰ ብከ እስመ ትጸልእ ምግባሮሙ ለኒቆላው
ያን በከመ አነ እጸልእ ፡ ዘቦ ዕዝን ሰሚዐ ለይስማዕ ።
፯ ምንተ ይቤ መንፈስ ቅዱስ ለአብያተ ክርስቲያናት ፡
ወለዘሞዐሰ እሁቦ ይብላዕ እምውስተ ዕፀ ሕይወት
ዘሀሎ ውስተ ገነቱ ለእግዚአብሔር ።
፰ ወጸሐፍ ሎቱ ለመልአከ ቤተ ክርስቲያን ዘሰሚርኔስ ፡
ከመዝ ይቤ ዘውእቱ ቀዳማዊ ወውእቱ ደኃራዊ
ዘሞተ ወሐይወ ።
፱ አአምር ሕማመከ ወኃጣይአከ ወባሕቱ ብዑል
አንተ ወፅርፈቶሙ ለእለ ይብሉ አይሁድ ንሕነ ወኢ
ኮኑ አላ ማኅበሩ ለሰይጣን እሙንቱ ፡ ኢትፍራህ
ምንተኒ በእንተ ዘሀለወከ ትሕምም ።
፲ እስመ ናሁ ሰይጣን ይወዲ እምኔክሙ ውስተ ሞቅሕ
ከመ ትትዓቀፉ ወተሐሙ ዐሡረ መዋዕለ ፡ ወኩን
መሃይምነ እስከ ለሞት ወእሁበከ አክሊለ ዘሕይ
ወት ፡ ዘቦ ዕዝነ ሰሚዐ ለይስማዕ ።
፲፩ ምንተ ይቤ መንፈስ ቅዱስ ለአብያተ ክርስቲያናት ፡
ወዘሰ ሞዐ ኢይመውት ዳግመ ሞተ ።
፲፪ ወጸሐፍ ሎቱ ለመልአከ ቤተ ክርስቲያን ዘጴርጋሞን
ከመዝ ይቤ ዘቦ ሰይፍ በሊሐ ዘክልኤ አፉሁ ።
፲፫ አአምር ኀበ ታኀድር እደ.ከ መንበሩ ለሰይጣን ወታ
ንጽዕ ስምየ ወኢክሕደከ ሃይማኖትየ ወበመዋዕል
ዘቀተልዎ በኀቤክሙ ለጻድቅየ መሃይምን በኀበ ያኀ
ድር ሰይጣን ።
፲፬ ወባሕቱ ቦ ዘአኀይስከ እስመ ሀለዉ ዝየ እለ ያጸንዑ
ትምህርቶ ለበላዓም መምህሩ ለባላቅ ወይወድዮ ዕቀ
ፍተ ቅድሜሆሙ ለደቂቀ እስራኤል ከመ ይብልዑ
ዝቡሐ ለአማልክት ወይዘምዉ ።
፲፭ ወእሉኒ ሀለዉ ኀቤከ እለ ያጸንዑ ትምህርቶሙ ለኒ
ቆላውያን ።
፲፮ ወይእዜኒ ነስሕ ወእመ አኮሰ እመጽእ ወእፀብአሙ
ፍጡነ በሰይፈ አፉየ ፡ ዘቦ ዕዝነ ሰሚዐ ለይስማዕ ።
፲፯ ምንተ ይቤ መንፈስ ቅዱስ ለአብያተ ክርስቲያናት ፡
ለዘሞዐ እሁቦ መና ዘኅቡእ ወእሁቦ መጽሐፈ ብር
ሃን ወውስተ ውእቱ መጽሐፍ ጽሑፍ ስም ሐዲስ
ዘአልቦ ዘየአምሮ ዘእንበለ ዘነሥኦ ።
፲፰ ወጸሐፍ ሎቱ ለመልአከ ቤተ ክርስቲያን ዘተያጥሮን ፡
ከመዝ ይቤ ወልደ እግዚአብሔር ዘአዕይንቲሁ ከመ
ነደ እሳት ወእገሪሁ ከመ ርስነ ብርት ሊባኖስ ።

በትሠራ መጥቼ መብራትህን ከመቅረዝዋ አጠ
ፋቃለሁ ።
ነገር ግን ይህ አለህ ፡ እኔ እንደምጠላ የኒቆላውያንን ፮
ግብር ትጠላለህና ፡ ጆሮ ያለው መስማትን ይስማ ።
መንፈስ ቅዱስ ለአብያተ ክርስቲያናት ምን አለ ? ፯
ድል ለነሣ ከፈጣሪዬ ገነት ውስጥ ካለው ዕፀ ሕይወት
ይበላ ዘንድ እሰጠዋለሁ ።
ለሰሚርኔስ ቤተ ክርስቲያን አለቃ ቀዳማዊ ደኃ ፰
ራዊ የሚሆን ሙቶ የተነሣው እሱ እንዲህ አለ
ብለህ ጻፍለት አለኝ ።
መከራህንና መቸገርህን ዐውቃለሁ ፡ ነገር ግን ባለ ፱
ጸጋ ነህ ፡ የሰይጣን ተባባሪዎች ናቸው እንጂ ሳይሆኑ
ምእመናን ነን የሚሉትን መንቀፍህን ዐውቃለሁ ፡
መከራ ትቀበል ዘንድ ስላለህ ምንም ምን አትፍራ ።
እነሆ ትጠራጠሩ ዘንድ ሰይጣን ከናንተ ወገን ወደ ፲
ግዞት ቤት ያገባልና ፡ ዓሥር ቀንም መከራ ትቀበላላ
ችሁ ፡ እስከ መሞት ደርሰህ የታመንክ ሁን ፡ የሕይ
ወትም አክሊል እሰጥሃለሁ ፡ ጆሮ ያለው መስማትን
ይስማ ።
መንፈስ ቅዱስ ለአብያተ ክርስቲያናት ምን አለ ? ፲፩
ድል የነሣ ሁለተኛ ሞት አይሞትም ።
ለጴርጋሞን ቤተ ክርስቲያን አለቃ የተሳለ ሁለት ፲፪
ልሳን ያለው ሰይፍ እሱ እንዲህ አለ ብለህ ጻፍለት
አለኝ ። ምዕ ፩ ፲፮ ። ኢያሱ ፭ ፲፫ ።
እጅህን ያኖርህባቸው ሰዎች የሰይጣን ማደሪያ እን ፲፫
ደሆኑ ዐውቃለሁ ስሜን አፅንተሃል ሃይማኖቴንም
አልካድክም ሰይጣን ያደረባቸው ሰዎች እውነተኛ
ታማኜን በናንተ ዘንድ በገደሉበት ወራት ።
ነገር ግን የምነቅፍብህ አለኝ ፡ የባላቅ መምህር የበለ ፲፬
ዓምን ትምህርት ያፀኑ ለጣኦት የተሠዋውን ይበሉ
ዘንድ በእስራኤል ልጆች ፊት መሰናከል የሚያኖሩ
ከዚያ አሉና ።
የኒቆላውያንን ትምህርት ያፀኑ እሊህም ከንተ ዘንድ ፲፭
አሉ ።
አሁንም ተመለስ ፡ ያለዚያ ግን ፈጥኜ መጥቼ ከፊ ፲፮
በሚወጣ ሰይፍ አጠፋቸዋለሁ ፡ ጆሮ ያለው መስማ
ትን ይስማ ። ኢሳ ፲፩ ፬ ።
መንፈስ ቅዱስ ለአብያተ ክርስቲያናት ምን አለ ? ፲፯
ድል ለነሣ የተሠወረ መናን እሰጠዋለሁ የብርሃን
መጽሐፍንም እሰጠዋለሁ በዚያም መጽሐፍ ውስጥ
ገንዘብ ከደረገው በቀር የማያውቀው የሌለ አዲስ
ስም ተጽፎአል ።
ለተያጥሮን ቤተ ክርስቲያን አለቃ ዐይኖቹ የእሳት ፲፰
ነበልባል እግሮቹም እንደ ደጋ ብረት ግለት የሆኑ
እሱ የእግዚአብሔር ልጅ እንዲህ አለ ብለህ ጻፍ
ለት አለኝ ። ምዕ ፩ ፲፬ ። ፲፬ ፲፭ ።

፲፱ አአምር ግብረከ ወተፋቅሮተከ ወሃይማኖተከ ወመ
ልእክተከ፥ ወትዕግሥተከ ፥ ወግብርከኒ ደኃሪት
ትበዝኅ እምነ ቀዳሚት ።
፳ ወባሕቱ ቦ ዘአኀይሰከ እስመ አርመምከ ላቲ ለኤል
ዛቤል ብእሲት እንተ ትብል ርእሳ ነቢይት ወኢኮነት
ወትሚህር በዘታስሕቶሙ ወታዜምዎሙ ለአግብር
ትየ ከመ ይብልዑ ዝቡሐ ለአማልክት ።
፳፩ ወወሀብክዋ መዋዕለ በዘትኔስሕ ወአበየት ነስሖ
እምነ ዝሙታ ።
፳፪ ወናሁ አገብኣ ውስተ ዘቀዳሚ ምስካብ ወለእለ ዘመዉ
ምስሌሃ ውስተ ዐቢይ ሥቃይ እመ ኢነስሐት እምነ
ምግባራ ።
፳፫ ወእቀትል ደቂቃ በሞት ወየአምሩ ኵሉ አብያተ
ክርስቲያናት ከመ አነ ውእቱ ዘእፈትን ልበ ወኵል
ያተ ወእፈድየክሙ ለለአሐዱ አሐዱ እምኔክሙ
በከመ ምግባሪክሙ ።
፳፬ ወለክሙኒ እብል ለእለ ተረፍክሙ ውስተ ተያጥሮን
ለእለ ኢልብክሙ ዝንቱ ትምህርት ለእለ ኢተአም
ርዋ ለጕኍሉተ ሰይጣን ዘይብል እወዲ ላዕሌክሙ
ክልኤ ክበደ ።
፳፭ ወባሕቱ ዘብክሙ አጽንዑ እስከ አመ እሣሃል ።
፳፮ ወለዘሞዐ ወዐቀበ ግብርየ ለዝሉፉ እሁቦ ሥልጣነ
ላዕለ አሕዛብ ።
፳፯ ወይርዕዮሙ በበትረ ሐፂን ወከመ ንዋየ ለብሐ
ይቀጠቅጦሙ ።
፳፰ በከመ አነ ነሣእኩ እምኀበ አቡየ ወእሁቦ ኮከበ
ጽባሕ ፥ ዘቦ ዕዝነ ሰሚዐ ለይስማዕ ።
፳፱ ምንተ ይቤ መንፈስ ቅዱስ ለአብያተ ክርስቲያናት ።

ምዕራፍ ፫ ።

፩ ወጸሐፍ ሎቱ ለመልአከ ቤተ ክርስቲያን ዘሰርዴ
ሲስን ፥ ከመዝ ይቤ ዘቦ ሰብዐቱ መንፈስ ዘእምኀበ
እግዚአብሔር ወሰብዐቱ ከከብ ።
፪ አአምር ግብረከ ከመ ስምከ ሕያው ወምውት አንተ፥
ትጋህ እንከ ወአፅንዖሙ ለእለ አልጸቁ ይሙቱ፥
እስመ ኢረከብኩ ግብረከ ፍጹመ በቅድመ እምላክየ።
፫ ወተዘከር እፎ ነሣእከ ወሰማዕከ ፥ ነስሕ እንከ ወእ
መሰ ኢተጋሀከ እበጽሐከ ግብተ ከመ ሰራቂ ወኢተ
አምር በአይ ሰዓት እመጽእ ላዕሌከ ።
፬ ወባሕቱ ብከ ኅዳጣን ሰብእ ውስተ ሰርዴስ እለ ኢገ
መኑ አልባሲሆሙ ምስለ አንስት ወየሐውሩ ምስ
ሌከ በንጽሕ ።
፭ ወሉዘሞዐ ከመዝ ልብሰ ንጹሐ ይደልዎ ወኢይደ



ሥራህን ፍቅር መያዝህን ሃይማኖትህን ተልእኮህ ፲፱
ንና ትዕግሥትህን በውቃለሁ፥ ከቀደሙቹቱ ሥራህ
የኋለኛይቱ የበዛች ትሆናለች ።
ነገር ግን የምነቀፍብህ አለኝ፡ ሳትሆን ነቢይ ነኝ የም ፳
ትል ለጣኦት የተሠዋውን ይበሉ ዘንድ ባለሟሎቼን
በምታስታቸውና በምታሴስናቸው ገንዘብ የምታስተ
ምር ኤልዛቤልን ዝም ብለሃታልና ። ፩ ነገ ፲፮ ፴፩ ።
ንስሐ በምትገባ ገንዘብ ዕድሜን ሰጠኋት ፥ ነገር ግን ፳፩
ከዝሙቷ አልመለስም አለች ። ሮሜ ፪ ፬-፭ ።
እነሆ ወደ ቀደመው መሬትነቷ እመልሳታለሁ ከክፉ ፳፪
ሥራዋ ካልተመለሰች ከሷ ጋር የሴሰኑትንም ለፅኑ
ፍዳ አሳልፌ እሰጣቸዋለሁ ።
ልጆቿንም በሞት አጠፋቸዋለሁ ልብንና ኵላሊ ፳፫
ትን የምመረምር እኔ እንደሆንሁ አብያተ ክርስቲ
ያናት ሁሉ ያውቃሉ ፥ ከናንተም ለያንዳንዱ እንደ
ሥራችሁ ፍዳችሁን እከፍላችኋለሁ ። ኤር ፲፯ ፲ ።
በተያጥሮን ለቀራችሁ ለናንተም ይህ ትምህርት ፳፬
ለሌላችሁ ሁለት ከባድ ነገሮችን አግብባችኋለሁ
የሚል የሰይጣንን ተንኰል ለማታውቁት እናገ
ራለሁ ።
ነገር ግን ይቀር እስክላችሁ ድረስ ያላችሁበትን አፅን ፳፭
ታችሁ ያዙ ።
ድል ነሥቶ ለዘለዓለሙ ሕጌን ለጠበቀ በአሕዛብ ፳፮
ላይ ሥልጣንን እሰጠዋለሁ ። ምዕ ፫ ፲፩ ።
በብረት ብትር ይጠብቃቸዋል፡ እንደ ሸክላ ዕቃም ፳፯
ይቀጠቅጣቸዋል ። ምዕ ፲፪ ፭ ።
እኔ ከባቴ ሥልጣንን እንደ ተቀበልኩ የንጋትን ፳፰
ከከብ እሰጠዋለሁ ፥ ጆሮ ያለው መስማትን ይስማ ።
መንፈስ ቅዱስ ለአብያተ ክርስቲያናት ምን አለ? ። ፳፱

ምዕራፍ ፫ ።

ለሰርዴሲስን የቤተ ክርስቲያን አለቃ ፍጹም መንፈስ ፩
ከእግዚአብሔር ዘንድ ያለው ሰበትንም ከከብ በቀኝ
እጁ ያለ እሱ እንዲህ አለ ብለህ ጻፍለት አለኝ ።
ስምህ ሕያው እንደሆነ አንተ ግን የሞትህ እንደ ፪
ሆንህ በሥራህ አውቃለሁ እንግዲህ ተግተህ ሊሞቱ
የቀረቡትን አፅናቸው በፈጣሪዬ ፊት ሥራህን
ፍጹም ሁኖ አላገኘሁትምና ። ቊ፡ ፲፱ ።
እንዴት ተቀበልህ እንዴትስ ሰማህ አስኪ አስተውል ፫
እንግዲህስ ንስሐ ግባ ያልተጋህ እንደሆነ ግን እንደ
ሌባ ድንገት እደርስብሃለሁ በማናቸውም ሰዓት እንድ
መጣብህ አታውቅም ። ፩ ተሰ፡ ፭ ፪ ።
ነገር ግን ከሴቶች ጋራ ልብሳቸውን ያላሳደፉ ከን ፬
ተም ጋራ በንጽሕና የሚኖሩ ጥቂት ሰዎች በሰርዴስ
አሉህ ። ይሁ፡ ፳፫ ።
ድል ለነሣም እንዲህ ንጹሕ ልብስ ይገባዋል በሙም ፭

ወይበክይዋ ወይላኅውዋ ወይብሉ አሌ ላ፡ አሌ ላ፡
ለሀገር ዐባይ እንተ እምኔሃ ብዕሉ ኵሎሙ እለ በሙ
አሕማር ውስተ ባሕር እምነ ክብራ፡ እስመ በአሐቲ
ሰዓት ማሰነት ።

፳ ለይትፌሣሕ ላዕሌሃ ሰማይ ወቅዱሳን ነቢያት ወሐዋ
ርያት እስመ ተበቀለ እግዚአብሔር በቀለክሙ ።

፳፩ ወነሥአ አሐዱ መልአክ ኀያል ወፁሩ እብነ ዐቢየ
ከመ እንተ ማኅረፅ ወወገረ ውስተ ባሕር፡ ወይቤ
ከመዝ ትትገደፍ ባቢሎን ሀገር ዐባይ ወኢትትረከብ
እንከ ።

፳፪ ወኢይሰማዕ በውስቴታ ቃለ መሰንቆት ወዕንዚራ
ወማኅሌት ወቃለ ቀርን ኢይሰማዕ በውስቴታ ወኵሉ
ኬንያ ወኵሉ ኪን ኢይትረከብ በውስቴታ፡ ወኢብ
ርሃነ ማኅቶት ወኢ ቃለ መርዓዊ ወመርዓት ኢይሰ
ማዕ በውስቴታ ።

፳፫ እስመ ሠየጥኪ መሳፍንተ ምድር እለ አስሐትኪ
ዮሙ በሥራይትኪ ለኵሉ አሕዛበ ምድር ።

፳፬ ወተረከበ በላዕሌኪ ደመ ነቢያት ወዘቅዱሳን ወዘኵ
ሎሙ እለ ተቀትሉ በውስተ ምድር በእንተ ስሙ
ለክርስቶስ ።

ምዕራፍ ፲ወ፱፡

፩ ወእምድኅረ ዝንቱ ተሰምዐ ቃል ዐቢይ እምሰማይ
ከመ ዘብዙኅ ሰብእ ወይብሉ ሃሌ ሉያ እስመ ስብ
ሐት ወፍርቃን ወኃይል ለአምላክነ ።

፪ እስመ ጽድቅ ወርትዕ ኵነኔሁ፡ እስመ ኰነና ለዐባይ
ዘማ እንተ አማሰነት ምድረ በዝሙታ ወተበቀለ ደመ
ኵሎሙ አግብርቲሁ እምእዴሃ ።

፫ ወይብሉ ዳግመ ሃሌ ሉያ ።

፬ ወፀርገ ጢስ ዘለዓለመ ዓለም፡ ወሰገዱ እልክቱ
ዕሥራ ወአርባዕቱ ሊቃናት ወእልክቱኒ አርባዕቱ
እንስሳሁ ለእግዚአብሔር ዘይነብር ዲበ መንበሩ
ቅዱስ ወይብሉ አሚን ሃሌ ሉያ ።

፭ ወወፅአ ቃል እምሰማይ እምውስተ መንበሩ ዘይ
ብል ሰብሑ ለአምላክነ ኵልክሙ አግብርቲሁ ወእለ
ትፈርህዎ ንኡሳኒክሙ ወዐቢይክሙ ።

፮ ወእምዝ ሰማዕኩ ቃለ ከመ ዘብዙኅ ሰብእ ወከመ
ቃለ ማይ ብዙኅ ወከመ ቃለ ነጐድጓድ ዐቢይ እንዘ
ይብሉ ሃሌ ሉያ እስመ ነግሠ እግዚአብሔር ዘኵሎ
ይመልክ ።

የተነሣ ከብረው የሚኖሩ፡ ከክብሯ ብዛት የተነሣ
በባሕር መርከብ የሚያኖሩ ሁሉ ለደጊቱ ሀገር ወዮ
ላት! ወዮላት! እያሉ ያዝኑላታል ያለቅሱላታል በአ
ንድ ሰዓት ጠፍታለችና ። ሕዝ ፳፯፡ ፳፱፡ ፴ ። ፩
ሳሙ ፬፡ ፲፪ ። ኢዮ ፪፡ ፲፪ ።

መላእክት፡ ቅዱሳን፡ ነቢያትና ሐዋርያት ደስ ይበላ ፳
ችሁ፡ እግዚአብሔር ስለናንተ ተበቀሎ ፈርዶላች
ኋልና ። ኢሳ ፵፬፡ ፳፫ ። መሰ ፫፡ ፴፩ ። ምሳ ፲፩፡ ፲ ።

ኃያል ሰሉ የሚሆን አንድ መልአክ ወፍጮ የሚያ ፳፩
ህል ታላቅ ድንጊያ አንሥቶ ከባሕር ጥሎ ደጊቱ
ሀገር ባቢሎን እንዲህ ትጠፋለች፡ እንግዲህ አትገ
ኝም ። ኤር ፶፩፡ ፷፫ - ፷፬ ።

በውስጧ የመሰንቆ የበገና የዘፈን ቃል አይሰማ ፳፪
ባትም የነጋሪት ድምፅም በውስጧ አይሰማም፡ የጥ
በብም ሁሉ ሠራተኛ በውስጧ አይገኝም ። የመብ
ራት ብርሃን አይገኝባትም፡ የሙሽራትና የሙሽራ
ድምፅ አይሰማባትም ። ኢሳ ፳፬፡ ፰ ። ኤር ፯፡ ፴፬ ።

በሥራይሽ ያሳትሺያቸው የምድርን መሳፍንቶች ፳፫
ለአሕዛብ ሸጠሺያቸዋልና ። ኤር ፯፡ ፴፬ ። ኤር ፴፫፡
፲፩ ። ፪ ነገ ፱፡ ፳፪ ። ምሳ ፲፯፡ ፪ ።

የነቢያትና የቅዱሳን ሐዋርያት በምድርም ስለ ክር ፳፬
ስቶስ ስም የሞቱ ሰዎች ሁሉ ደም ባንቺ ላይ ተገኘ።
ኤር ፶፩፡ ፵፱ ።

ምዕራፍ ፲፱ ።

ከዚህ በኋላ እንደ ብዙ ሰው ድምፅ ያለ ታላቅ ቃል ፩
ከሰማይ ተሰማ፡ ቀድሞ ለነበረ እንግዲህም ለሚኖር
ለአምላካችን መድኃኒት የመባል ምስጋና ኃይል ይገ
ባል ሲሉ ተሰማ ። መዝ፡ ፫ ፰፡ ምዕ፡ ፬ ፲፩ ።

ፍርዱ ቅን እውነት ነውና የወዳጆቹን ሁሉ ደም ፪
ከእጅዋ ተቀብሎ በዝሙቷ ምድርን ባሳደፈች በታ
ላቂቱ ዘማ ፈርዶባታልና ። ምዕ፡ ፲፮ ፯ - ፲ ።

ዳግመኛም ቀድሞ ለነበረው እንግዲህም ለሚኖረው ፫
ለአምላካችን ምስጋና ይገባል ሲሉ ። ኢሳ፡ ፴፬ ፲፡

የማያቋርጥ ጢስ ወጣ እሊያ ሃያ አራቱ አለቆችና ፬
እነዚያ አራቱ እንስሶች በከበረ ዙፋኑ ላይ ተቀምጠ
ላለ እግዚአብሔር ቀድሞ የነበረ እንግዲህም የሚ
ኖር ዘለዓለማዊ መባል በእውነት ይገባዋል እያሉ
ሰገዱለት ። ነህ፡ ፰ ፲፫ ።

ከዙፋኑ በታች ካለ ከሰማይም ትንሹም ትልቁም ፭
የምትፈሩት ባለሟሎቹ ሁላችሁ አምላካችንን አመስ
ግኑ የሚል ቃል ከወደ ሰማይ ተሰማ ። መዝ፡ ፻፴፬ ፩ ።

ከዚህ በኋላ ቀድሞ ለነበረው እንግዲህም ለሚኖረው ፮
ለአምላካችን ምስጋና ይገባል ሲሉ እንደ ብዙ ሰው
ድምፅ እንደ ውኃ ፏፏቴና እንደ ታላቅ ነጐድጓድ
ያለ ቃል ሰማሁ፡ ሁሉን የሚገዛ እግዚአብሔር ነግ
ሦዋልና ። ሕዝ፡ ፩ ፳፬ ።

፯ ለንትፈሣሕ ወንትኅሠይ ወነሀብ ሎቱ ስብሐተ እስመ
በጽሐ መርዓ በግዑ ፡ ወብእሲቱኒ ድሉት ይእቲ ።

፰ ወተውህበ ላቲ ከመ ትልበስ ሚላተ ብርሃን ንጹሐ
እስመ ውእቱ ሚላት ጽድቆሙ ለቅዱሳን ።

፱ ወይቤለኒ ጸሐፍ ብፁዓን እለ ተጸውዑ ውስተ በዓለ
መርዓ በግዑ እስመ ዝንቱ ቃለ ጽድቅ ዘእግዚአብ
ሔር ውእቱ ።

፲ ወወደቁ ኀበ እገሪሁ ወሰገድኩ ሎቱ ወይቤለኒ ዑቅ
ዮጊ ኢትስግድ ሊተ እስመ አነሂ ገብር ዘከማከ ወዘ
ምስሌከ ወምስለ አኀዊከ ነቢያት እለ የዐቅቡ ሕጎ
ለኢየሱስ ፡ ወበሕቱ ለእግዚአብሔር ንስግድ ኵሉነ
እስመ ሕጉ ለኢየሱስ መንፈሰ ትንብዩ ።

፲፩ ወእምዝ ተርኅወ ሰማይ ወዐዕአ ፈረስ ፀዓዳ ወዘይ
ጼዐኖ ስሙ መሃይምን ወጻድቅ ወዘበጽድቅ ይኬንን
ወይፀብእ ።

፲፪ ወአዕይንቲሁ ከመ ነደ እሳት ወዲበ ርእሱ አክሊል
ወጽሑፍ ውስተ ቀጸላሁ አስማት ዘአልበ ዘየአምሮ
ዘእንበለ ውእቱ ባሕቲቱ ።

፲፫ ወይለብስ ልብሰ ዘንዙኅ በደም ወሰመዩ ስሞ ቃለ
እግዚአብሔር ።

፲፬ ወሐራ ሰማይ ይተልውዎ በአፍራስ ፀዓድው ወይለ
ብሱ ሚላተ ብርሃን ንጹሐ ።

፲፭ ወይወጽእ እምነ አፉሁ ሰይፍ በሊሕ ዘበቱ ይቀሥ
ፎሙ ለአሕዛብ ወውእቱ ይርዕዮሙ በበትረ ሐፂን
ወውእቱ ይከይዳ ለምክያደ ወይነ ሕምዘ መዓቱ ለእ
ግዚአብሔር ዘኵሎ ይመልክ ።

፲፮ ወጽሑፍ ላዕለ ልብሱ ወውስተ ገቦሁ ስም ዘይብል
ንጉሠ ነገሥት ወእግዚአ አጋእዝት ።

፲፯ ወእምዝ ቆመ አሐዱ መልአክ ውስተ ፀሐይ ወይጸ
ርሕ በቃል ዐቢይ ወይቤ ለኵሉ አዕዋፍ ዘይሠርር
ውስተ ማእከለ ሰማይ ንዑ ተጋብኡ ውስተ በዓሉ
ለእግዚአብሔር ዐቢይ ።

፲፰ ከመ ትብልዑ ሥጋ ነገሥት ወሥጋ መላእክት ወሥጋ
ዕኑዓን ወሥጋ አፍራስ ወዘእለ ይጼዐንዎሙ ወሥጋ
ኵሉ አግብርት ወግዕዛን ወንኡሳን ወዐቢያን ። [sic: ኵሉ አግአዚ ወገብር ወዘንኡስ ወዘዐቢይ]

፲፱ ወእምዝ መጽአ ዝክቱ አርዌ ወነገሥተ ምድር ወሠ
ራዊቶሙ ተጋብኡ ምስሌሁ ከመ ይፅብእዎ ለውእቱ
አርዌ ዘይጼዐን ላዕለ ፈረስ ፀዓዳ ወለሠራዊቱ ።

፳ ወእምዝ አኀዝዎ ለዝኩ አርዌ ወለሐሳዌ ነቢዩ ዘገ
ብረ ተአምራተ በቅድሜሁ በዘያስሕቶሙ ለእለ
ጸሐፉ ማኅተመ ስሙ ለውእቱ አርዌ ወሰገዱ ሎቱ

ደስ ይበለን ደስ ብሎንም ለርሱ ምስጋና እናቅርብ ፯
የበጉ ሠርግ ደርሷልና ሴቲቱም ለሠርጉ የተዘጋጀች
ናት ። ኢሳ፡ ፶፬ ፩፫ ፤ ማቴ፡ ፳፪ ፪ ፤ ፪ ቆሮ፡ ፲፩ ፪ ።
የብርሃን ነጭ ሐር ትለብስ ዘንድ ተሰጣት ይኸውም ፰
ነጭ ሐር የቅዱሳን ክብራቸው ነው ። መዝ፡ ፵፭ ፲፫ ።
ወደ በጉ ሠርግ የተጠሩ የተመሰገኑ ናቸው ብለህ ፱
ጻፍ አለኝ፡ ይህ የእውነት ቃል የእግዚአብሔር
ነውና ። ሉቃ ፡ ፲፬ ፲፭ ።
ከእግሩም ወድቄ ሰገድኩለት እኔም የኢየሱስን ሕግ ፲
ከሚጠብቁ ወንድሞችህ ነቢያትና ካንተ ጋራ እንዳ
ንተ ተገዥ ነኝና ለኔ እንዳትሰግድ ዕወቅ አለኝ ሁላ
ችን ለእግዚአብሔር እንስገድ እንጂ ትንቢትን የሚ
ያናግር መንፈስ መስጠት ለኢየሱስ ልማዱ ነውና ።
ምዕ፡ ፳፪ ፰ ፤ ግብ፡ ሐዋ፡ ፲ ፳፮ ፤ ፩ ዮሐ፡ ፭ ፲ ።
ከዚህ በኋላ ሰማይ ተከፈተ አምበላይ ፈረስም ወጣ ፲፩
የተቀመጠበትም የታመነ እውነተኛ ይባላል ፡ በእውነ
ትም ፈርዶ የሚያጠፋ ነው ። ኢሳ፡ ፲፩ ፬፤ ዮሐ፡ ፲፬ ፯ ፤
ዓይኖቹም እንደ እሳት ነበልባል ናቸው ፡ በራሱም ፲፪
ላይ አክሊል ደፍቷል በአክሊሉም ላይ ከሱ ብቻ
በቀር ሌላ የሚያውቀው የሌለ ስም ተጽፏል ።
ኢሳ፡ ፱ ፯ - ፯ ። ምዕ፡ ፪ ፲፰ ፤
ደም የተረጨ ልብስም ለብሷል ስሙንም የእግዚአ ፲፫
ብሔር ቃል ይሉታል ። ኢሳ፡ ፷፫ ፪ - ፫ ፤ ዮሐ፡ ፩ ፩ ።
የሰማይ ጭፍሮችም በአምበላይ ፈረሶች ተቀም ፲፬
ጠው ንጹሕ የብርሃን ነጭ ሐር ለብሰው ይከተሉ
ታል ። ዳን፡ ፲ ፯ ፤ ምዕ፡ ፬ ፬ ፤ ማቴ፡ ፲፯ ፪ ።
ከፉም አሕዛብን የሚቀጣበት የተሳለ ሰይፍ ይወጣል ፲፭
እሱም በብረት ብትር ይጠብቃቸዋል ሁሉን የሚገዛ
የእግዚአብሔር የቍጣው መርገዝ ወይን ያለበት ዓው
ድማን ተረግጧል ። መዝ፡ ፪ ፱ ፤ ምዕ፡ ፩ ፲፯ ።
በልብሱ ላይና በጐኑ ውስጥ የጌቶች ጌታ ፡ የንጉ ፲፮
ሦች ንጉሥ ፡ የሚል ስም ተጽፏል ። ዳን፡ ፪ ፵፯ ።
ከዚህ በኋላ አንድ መልአክ በፀሐይ ቁሞ በሰማይና ፲፯
በምድር መካከል ለሚበሩ ወፎች ወደ ታላቁ ወደ
እግዚአብሔር በዓል ኑ ተሰብሰቡ እያለ በታላቅ ቃል
ይጮኻል ። ሕዝ፡ ፴፱ ፬ ፡ ፲፯ ።
የነገሥታቱን ሥጋ የአለቆቹንና የአርበኞቹን ሥጋ ፲፰
የፈረሶችንና የተቀመጡባቸውን ሥጋ የገዢውንና
የተገዢውን የታላቁንና የታናሹን ሁሉ ሥጋ ትበሉ
ዘንድ ።
ከዚህ በኋላ ያ አውሬ መጣ፡ የምድር ነገሥታትና ፲፱
ሠራዊቶቻቸውም በአምበላይ ፈረስ ላይ ተቀምጦ
ያለ እሱን ከሠራዊቱ ጋር ይወጉት ዘንድ ከርሱ ጋር
ተሰበሰቡ ። ምዕ፡ ፲፮ ፲፮ ።
ከዚህ በኋላ ያን አውሬንና የስሙን ምልክት ጽፈው ፳
ለርሱና ለምስሉ የሰገዱትን በሚያስቷቸው ገንዘብ
በፊቱ የምታት ተአምራት ያደረገው ሐሰተኛውን

ወለምስሉ ፡ ወወደይዎሙ ሕያዋኒሆሙ ውስተ ዐዘ
ቅተ እሳት ዘይነድድ በተይ ።
፳፩ ወለእለሰ ተርፉ ቀተሎሙ በሰይፈ ዝክቱ ዘይጼዐን
ላዕለ ፈረስ ፀዓዳ እንተ ይወፅእ እምአፉሁ ሰይፍ
በሊሕ፡ወጸግቡ ኵሉ አዕዋፈ ሰማይ እምነ ሥጋሆሙ።

ምዕራፍ ፳ ፡

፩ ወእምዝ ወረደ ካልእ መልአክ እምሰማይ ወይፀውር
መራኁተ ዐሐይ ወዐበይት መዋቅሕት ውስተ እዴሁ።

፪ ወአኀዞ ለዝክቱ አርዌ ዘውእቱ ቀዳማዊ ወውእቱ
ጋኔን ሰይጣን ።

፫ ወአሠሮ ፲፻ተ ዓመተ ፡ ወአውደቆ ውስተ ማዕምቅ
ወዐፀወ ላዕሌሁ በማኅተም ከመ ኢያስሕት አሕዛበ
እስከ ይትፌጸም ዝንቱ ፲፻ ዓመት ፡ ወእምድኅረ
ዝንቱ ሀለዎ ይትፈታሕ ኅዳጠ መዋዕለ ።
፬ ወእምዝ ርኢኩ መናብርተ ወነበረ ላዕሌሆሙ ወልደ
እጓለ እመሕያው ወአግብአ ሎሙ ፍትሐ በእንተ
ስሙ ለኢየሱስ ወበእንተ ቃለ እግዚአብሔር፡ ወእ
ለሰ ኢሰገዱ ለዝክቱ አርዌ ወኢለምስሉ ወኢጸሐፉ
ትእምርቶ ውስተ ፍጽሞሙ ወኢውስተ እደዊሆሙ
እሙንቱ የሐይዉ ወይነግሡ ምስለ ክርስቶስ ፲፻
ዓመተ ።
፭ ወባዕዳንሰ ምውታን ኢይትነሥኡ እስከ አመ ይት
ፌጸም ዝንቱ ፲፻ ዓመት ። ወዛቲ ይእቲ ቀዳሚት
ሕይወት ።
፮ ብፁዕ ወቅዱስ ውእቱ ዘረከበ ክፍለ በይእቲ ዕለት
እንተ ትቀድም መጺአ እስመ አልቦ እንከ ዳግመ
ሥልጣነ ሞት ላዕለ እሉ እስመ ይከውኑ ካህናቲሁ
ለእግዚአብሔር ወለክርስቶስ ወይነግሡ ምስሌሁ
፲፻ ዓመተ ።
፯ ወሶበ ኀልቀ ፲፻ ዓመት ይትፈታሕ ሰይጣን እምነ
ሞቅሑ ።
፰ ወይወፅእ ያስሕቶሙ ለአሕዛብ እለ ውስተ አርባ
ዕቱ መዓዝኒሃ ለምድር ወያስተጋብኦሙ ለጎግ ወለ
ማጎግ ከመ ያስተቃትሎሙ ወኍልቆሙሰ ከመ ኆፃ
ባሕር ።
፱ ወዐርጉ ውስተ ስፍሐ ለምድር ፡ ወዐገትዋ ለትዕይ
ንቶሙ ለቅዱሳን ወለሀገር ቅድስት ፡ ወእምዝ ወረ
ደት እሳት እምሰማይ እምኀበ እግዚአብሔር ወበ
ልዐቶሙ ።
፲ ወለዝክቱኒ ሰይጣን ዘያስሕቶሙ ወደይዎ ውስተ
ዐዘቅተ እሳት ወተይ ኀበ ሀሎ ዝክቱ አርዌ ወሐሳዌ
ነቢይ ከመ ይደየኑ መዐልተ ወሌሊተ እስከ ለዓለመ
ዓለም ።
፲፩ ወእምዝ ርኢኩ መንበረ ዐቢየ ወፀዓዳ ወእምዘ ይነ



ነቢይ ይዘው በሕይወታቸው ሳሉ ከዲኝ ጋር እሳት
በሚነድበት ጕድጓድ ውስጥ ጣሉዋቸው ።
የቀሩትን ግን በአምበላይ ፈረስ ላይ ከተቀመጠው ፳፩
አፍ በምትወጣ ሰይፍ ገደልዋቸው የሰማይ ወፎ
ችም ሁሉ ከሥጋቸው በልተው ጠገቡ ።

ምዕራፍ ፳ ።

ከዚህ በኋላ ሌላ መልአክ ከሰማይ ወረደ፡ የምድር ፩
መክፈቻን ይዚል ታላላቅ እግር - ብረቶችንም በጁ
ተይዘዋል ። ምዕ፡ ፩ ፲፰ ።
ያን የፊተኛውን አውሬ ያዘው ይኸውም ጋኔን የተ ፪
ባለው ሰይጣን ነው ይዞም ሺሕ ዓመት አጋዘው ።
፪ ጴጥ፡ ፪ ፬፡ ምዕ፡ ፲፪ ፱ ።
ሺሕ ዓመት እስኪፈጸም ድረስ አሕዛብን እንዳያስት ፫
በጥልቅ ጕድጓድ ጥሎ በስኑ ቍልፍ ዘጋበት ኋላ ግን
ጥቂት ቀን ይፈታ ዘንድ አለው ። ዳን፡ ፯ ፲፯ ።

ከዚህም በኋላ ዙፋኖች ተዘርግተው የሰው ልጅ በላ ፬
ያቸው ተቀምጦ አየሁ ፡ ስለ ኢየሱስና ስለ እግዚአ
ብሔር ቃል ስለ ሞቱ ሰዎች ነፍስ ቀን ፍርድን ፈረ
ደላቸው ፡ ለዚያ አውሬና ለምስሉ ያልሰገዱ የስሙ
ንም ምልክት በግንባራቸው ያልጻፉ በእጃቸው
ያልተከተቡ እሊህ ተነሥተው ከክርስቶስ ጋር ሺሕ
ዓመት ይነግሣሉ ። ዳን ፯ ፱ ፡ ፳፪ ፳፯ ።
የቀሩት ሙታን ግን ይህ ሺሕ ዓመት እስኪፈጸም ፭
ድረስ አይነሡም ፡ መጀመሪያዪቱ ትንሣኤ ይህች
ናት ። ፩ ቆሮ ፲፭ ፳፫ ። ፩ ተሰ ፬ ፲፯ ።
አስቀድሞ በምትመጣ በዚያች ቀን የመንግሥት ዕድል ፮
ያገኘ ሰው ክቡር ምስጉን ነው ፡ ዳግመኛ በኒያ ላይ
የሞት ሥልጣን የለምና ፡ የእግዚአብሔርና የክርስ
ቶስ አገልጋዮች ሆነው ከርሱ ጋር ሺሕ ዓመት
ይነግሣሉና ። ኢሳ ፷፩ ፯ ። ምዕ ፳፩ ፰ ።
ሺሕ ዓመት በተፈጸመ ጊዜ ሰይጣን ከእስራቱ ፯
ይፈታል ።
በምድር በአራቱ መዓዝን ያሉት አሕዛብን ያስታ ፰
ቸው ዘንድ ይወጣል ፡ ጎግ ማጎግንም ያዋጋቸው
ዘንድ ይሰበስባቸዋል ፡ ቍጥራቸውም እንደ ባሕር
አሸዋ ነው ። ሕዝ ፴፰ ፪ ። ፩ ጴጥ ፭ ፰ ።
ወደ ሰፊም ሜዳ ወጥተው የቅዱሳን ከተማ የሆነች ፱
ቅድስት ሀገርን ይከቧታል ፡ ከዚህ በኋላ ከእግዚአብ
ሔር ዘንድ ታዝዛ ከሰማይ እሳት ወርዳ ትፈጃቸዋ
ለች ። ኢሳ ፰ ፰ ። ሕዝ ፴፰ ፳፪ ። ሕዝ ፴፱ ፯ ።
ያነንም ያሳታቸውን ሰይጣን ለዘለዓለሙ ሌትና ቀን ፲
እንዲሠቃዩ ያ አውሬና ሐሰተኛው ነቢይ ወዳሉበት
በዲኝና በእሳት ጕድጓድ ውስጥ ጣሉት ። ምዕ ፲፱ ፳።

ከዚህ በኋላ ታላቅና ነጭ ዙፋንን አየሁ ፡ በላዩም ፲፩

ብር ዲቤሁ ጕዩ እምቅድመ ገጹ ሰማይ ወምድር ወኢተረክበ መካን ።
፲፪ ወእምዝ መጽኡ ኵሎሙ ምዉታን ዐቢያን ወንኡሳን ወቆሙ ቅድመ መንበሩ ፡ ወከሠቱ ኵሉ መጻሕፍተ ፡ ወለመጽሐፈ ሕይወትሰ እንተ በሕቲታ ከሠትዋ ወተኰነኑ እልክቱ ምዉታን በከመ ጽሑፍ ውስተ ዝንቱ መጽሐፍ በከመ ገብሩ ።
፲፫ ወአግብአት ባሕርኒ ኵሎ ምዉታነ እለ ውስቴታ ወአግብኡ ሲኦል ወሞት ዘኀቤሆሙ ምውታን ፡ ወአግብአት ምድርኒ እለ ሀለዉ ውስቴታ ምዉታነ ፡ ወተኰነኑ ኵሎሙ በከመ ምግባሮሙ ።
፲፬ ወወደይዎሙ ለሲኦል ወለሞት ውስተ ዐዘቅተ እሳት ዘምልእት ተየ ፡ ወሞትሰ ዳግም ገሃነም ዘእሳት ውእቱ ።
፲፭ ወለኵሉ ዘኢይትረከብ ጽሑፍ ውስተ መጽሐፈ ሕይወት ይወድይዎ ውስተ ገሃነም ዘእሳት ።

ምዕራፍ ፳ወ፩ ፤

፩ ወእምዝ ርኢኩ ሰማየ ሐዲሰ ወምድረ ሐዳሰ እስመ ሰሰለ ሰማይ ቀዳማዊ ወምድርኒ ቀዳሚት ፡ ወባሕርኒ ተሰዐረት እንከ ።

፪ ወለሀገርኒ ቅድስት ሐዳስ ኢየሩሳሌም ርኢክዋ ወረደት እምሰማይ እምኀበ እግዚአብሔር ወድሉት ይእቲ ከመ መርዓት ሥርጉት ለምታ ።

፫ ወሰማዕኩ ቃለ ዐቢየ እምሰማይ ዘይብል ፡ ናሁ ቅድሳቱ ለእግዚአብሔር ምስለ እጓለ እመሕያው ኀደረት ምስሌሆሙ ፡ እሙንቱኒ ይከውንዎ ሕዝበ ወውእቱኒ ይከውኖሙ አምላኮሙ ወይሄሉ እግዚአብሔር ምስሌሆሙ ።
፬ ወያሴስል አንብዐ እምአዕይንቲሆሙ ወአልቦ እንከ ሞት ወኢላሕ ወኢገዓር ወኢሕማም አልቦ እንከ ፡ እስመ ኀለፈ ዘቀዳሚ ሥርዓት ወናሁ ተሐደሰ ኵሉ ።

፭ ወይቤ ዘይነብር ዲበ መንበሩ ናሁ እገብር ኵሎ ሐዲሰ ፡ ወይቤለኒ ጸሐፍ እስመ ዝንቱ ቃል እሙን ዘበጽድቅ ይከውን ።

፮ አነ ውእቱ አልፋ ወኦ ወአነ ቀዳማዊ ወአነ ደኃራዊ ወአንሰ ለዘጸምአ እሁብ ይስተይ እምነቅዐ ማየ ሕይወት በከንቱ ።

፯ ወዘሰ ሞአ ይወርሶ ለዝንቱ ወእከውኖ ሎቱ አምላከ ወውእቱኒ ይከውነኒ ወልደ ።

፰ ወእለሰ ይፈርህዎ እንዘ የአምኑ ወያጌምኑ ሥጋሆሙ

ላይ ተቀምጦ ከለው ከፊቱ መገለጽ የተነሣ ሰማይና ምድር ሸሹ ፡ በታም አላገኙም ። ዳን ፪ ፴፭ ።
ከዚህ በኋላ ታላቁም ታናሹም ሙታን ሁሉ ተነሥተው በዙፋኑ ፊት ቆመው መጻሕፍቱን ሁሉ ገለጡ ፡ የሕይወት መጽሐፍን ግን ለብቻዋ ገለጧት ፡ እነዚያም ሙታን በዚህ መጽሐፍ እንደ ተጻፈ እንደየሥራቸው ተፈረደባቸው ። ዳን ፯ ፲ ። ፪ ቆሮ ፭ ፲ ። ፲፪
በሕርም በውስጧ ያሉትን ሙታን መለሰች ፡ መቃብርና ሞትም ከነሱ ዘንድ ያሉ ሙታንን መለሱ ፡ ምድርም በውስጧ ያሉትን ሙታን መለሰች ሁሉም እንደየሥራቸው ተፈረደባቸው ተፈረደላቸው ። ፲፫
መቃብርንና ሞትንም ዲኝ በተመላች በእሳት ጕድጓድ ውስጥ ጣሉዋቸው ፡ ሁለተኛው ሞት ግን ገሃነመ እሳት ነው ። ፩ ቆሮ ፲፭ ፳፯ ፡ ፶፩ ፶፭ ። ፲፬
በሕይወት መጽሐፍ ውስጥ ተጽፎ ያልተገኘውን ሁሉ በገሃነመ እሳት ይጥሉታል ። ምዕ ፲፱ ፳ ። ፲፭

ምዕራፍ ፳፩ ፤

ከዚህ በኋላ አዲስ ሰማይ አዲስ ምድር አየሁ ፡ የቀደመው ሰማይና የቀደመችው ምድር አልፈዋልና ፡ ባሕርም ያን ጊዜ ታልፋለች ። ኢሳ ፶፯ ፳ ፡ ኢሳ ፷፭ ፡ ፲፯ ፡ ፪ ጴጥ ፫ ፲፫ ። ፩
የከበረች ሐዲሲቱ ሀገር ኢየሩሳሌምም ከእግዚአብሔር ዘንድ ከሰማይ ስትወርድ አየኋት ፡ ሙሽራ ለባሏ ያጌጠች እንደ ሆነች አጊያም ዝግጁ ናት ። ኢሳ ፶፪ ፡ ፩ ። ኢሳ ፶፬ ፡ ፭ ። ፪ ቆሮ ፲፩ ፡ ፪ ። ፪
እነሆ የእግዚአብሔር ክብሩ ለሰው ተሰጠች የሚል ታላቅ ድምፅ ከወደ ሰማይ ሰማሁ ፡ እነሱ ወገኖቹ ይሆናሉ ፡ እሱም አምላካቸው ይሆናል ፡ እግዚአብሔር አድሮባቸው ይኖራል ። ዘሌ ፳፮ ፡ ፲፩ ። ሕዝ ፴፯ ፡ ፳፯ ። ምዕ ፯ ፡ ፲፯ ። ፪ ቆሮ ፮ ፡ ፲፯ ። ፫
ከዓይናቸው ዕንባን ያርቃል ፡ እንግዲህ ሞት ፡ ልቅሶ ፡ ጩኸት መከራ የለባቸውም ፡ የቀድሞ ሥርዓት አልፎ እነሆ ሁሉ ታድሷልና ። ኢሳ ፳፭ ፡ ፰ ። ኢሳ ፴፭ ፡ ፲ ። ፩ ቆሮ ፲፭ ፡ ፳፮ ፡ ፶፬ ። ፬
በዙፋኑ ላይ የተቀመጠው እሱ እነሆ ሁሉን ሐዲስ አደርገዋለሁ ብሏልና ፡ ይህ ቃል በእውነት እንደ ሚሆን የታመነ ነውና ጻፍ አለኝ ። ኢሳ ፵፫ ፡ ፲፱ ፡ ፪ ቆሮ ፡ ፭ ፡ ፲፯ ፡ ፳፩ ። ምዕ ፬ ፡ ፪ ። ፭
ቀዳማዊ ደኃራዊ የምሆን አልፋ ፡ ኦ ፡ እኔ ነኝ ፡ ለተጠማ ከሕይወት ውኃ ምንጭ ይጠጣ ዘንድ ያለ ዋጋ እሰጠዋለሁ ። ኢሳ ፲፪ ፡ ፫ ። ዮሐ ፯ ፡ ፴፯ ። ምዕ ፳፪ ፡ ፲፯ ። ፮
ድል የነሣም ይህን ይወርሰዋል እኔ አባት እሆነዋለሁ እሱም ልጅ ይሆነኛል ። ዘካ ፰ ፡ ፰ ። ሮሜ ፰ ፡ ፲፯ ፡ ፴፪ ፡ ምዕ ፪ ፡ ፯ ፡ ፲፩ ። ፯
ሳያምኑ የሚፈሩት ግን ራሳቸውን የሚያሳድፉ ፰

ወይቀትሉ ወይዜምዉ ወይገብሩ ሥራየ ወያመልኩ
አማልክተ ወኵሎ ሐሰተ ይከውን ምንዳቤሆሙ ገሃ
ነም ዘእሳት ወተይ ወዝንቱ ውእቱ ዳግም ሞት ።

፱ ወመጽአ አሐዱ እምነ እልክቱ ሰብዓቱ መላእክት
እለ ይፀውሩ ሰብዓተ ጽዋዓተ እለ ምሉኣን ሰብዓተ
መቅሠፍተ ደኃርየተ ወተናገረ ምስሌየ ወይቤለኒ
ነዓ አርኢከሃ ለመርዓት ለብእሲተ በግዑ ።
፲ ወወሰደኒ መንፈስ ውስተ ደብር ዐቢይ ወነዋኅ ወአ
ርአየኒሃ ለሀገር ቅድስት ኢየሩሳሌም እንተ ትወርድ
እምሰማይ እምኀበ እግዚአብሔር ።

፲፩ ወስብሐተ እግዚአብሔር ላዕሌሃ፡ ወከዋክብቲሃኒ
ይመስሉ ከመ ዕንቍ ክቡር ወዕዕዱት ይእቲ ከመ
ባሕርይ ።
፲፪ ወዓበይ ዓረፍታ ወነዋኅ ጥቅማ ወባቲ ዐሠርቱ ወክ
ልኤቱ አናቅጽ ወውስተ አናቅጺሃ ዐሠርቱ ወክል
ኤቱ መላእክት ወጽሑፋን አስማት ዘዐሠርቱ ወክል
ኤቱ ሕዝበ እስራኤል ።
፲፫ ወውስተ አናቅጽ ጽባሓውያን ሠለስቱ፡ ወውስተ
አናቅጽ ዐረባውያን ሠለስቱ፡ ወውስተ አናቅጽ ሰሜ
ናውያን ሠለስቱ፡ ወውስተ አናቅጽ ደቡባውያን
ሠለስቱ ።
፲፬ ወዐሠርቱ ወክልኤቱ መሠረታቲሃ ለዓረፍተ ሀገራ
ወጽሑፍ ውስቴቶን አስማተ ዐሠርቱ ወክልኤቱ
ሐዋርያተ በግዑ ።
፲፭ ወዝክቱ ዘይትናገር ምስሌየ ይፀውር ኀለተ ወርቅ
በዘበቱ ይሚጥና ለይእቲ ሀገር ወለአናቅጺሃ ወለዓ
ረፋቲሃ ።
፲፮ ወርብዕት ይእቲ ሀገር በእምጣነ ኑኃ ወግድማ፡ ወመ
ጠና ለይእቲ ሀገር በውእቱ ኀለት ወከነ እምጣኒሃ
ዐሠርተ ወክልኤተ ምእተ ኑኃ ወግድማ ወቆማኒ
ዕሩይ ።

፲፯ ወእምዝ መጠነ ዓረፋቲሃ ምእት ወአርባዓ ወአርባ
ዕቱ በእመት ሰብእ ዘውእቱ አሐዱ በእመት መልአክ።

፲፰ ወውስተ ርእሰ ዓረፍታ ለይእቲ ሀገር በዕንቈ ኢያስ
ጲድ ወበያክንት ወትመስል ሀገራ ከመ ዘበወርቅ
ንጹሕ ግብረታ ።
፲፱ ወመሠረተ ዓረፍት ሀገራ ከመ ማኅው ፀዓዳ ሥር
ጉት በኵሉ ዕንቍ ክቡር፡ ወቀዳሚት መሠረት በኢ
ያስጲድ፡ ወካልእት በሰንፔር፡ ወሣልስት በኬልቄ
ዶን፡ ወራብዕት በዘመረግድ ።

ነፍስ የሚገድሉ፡ የሚሴስኑ፡ ሥራይ የሚያደርጉ፡
ጣዖታትን የሚያመልኩ፡ ሐሰትን ሁሉ የሚናገሩ
ቅጣታቸው እሳትና ዲኝ ያለበት ገሃነም ይሆናል፡
ሁለተኛ ሞት ይህ ነው። ፩ ቆሮ ፮፡ ፱ ። ኤፌ ፭፡
፭ ። ፩ ጢሞ ፩፡ ፱ ። ዕብ ፲፡ ፴፰ - ፴፱ ። ምዕ ፳፪፡ ፲፭ ።
የኋለኞችን ሰባት መቅሠፍቶች የተመሉ ሰባት ጽዋ ፱
ዎችን ከያዙ ከነዚያ ሰባቱ መላእክት አንዱ መጥቶ
ከኔ ጋር ተነጋገረ፡ በጉ የተሠዋላትን ሙሽራ ሴት ና፡
ላሳይህ አለኝ ። ምዕ ፲፭፡ ፩ ። ፯፡ ፯ ። ምዕ ፲፱፡ ፯ ።
መንፈስም ወደ ታላቅና ረጅም ተራራ ወስዶ ከእግ ፲
ዚአብሔር ዘንድ ከሰማይ የምትወርደውን ቅድስት
ሀገር ኢየሩሳሌምን አሳየኝ የእግዚአብሔርም ብር
ሃን ሰፍሮበታል ።
ከዋክብቶቿም ክቡር ዕንቍን ይመስላሉ፡ እንደ ዕን ፲፩
ቍም የጸሩ ናት ። ቍ ፳፫ ። ሕዝ ፵፫፡ ፴፭ ።

አርከኗ ታላቅ ነው፡ ቅጥሯም ረጅም ነው፡ ዓሥራ ፲፪
ሁለት ደጃፎች አሏት፡ በደጃፎቿም ዓሥራ ሁለት
መላእክት ቆመዋል፡ የዓሥራ ሁለቱ ነገደ እስራኤል
ስም ተጽፎበቸዋል ።
በምሥራቅ በሉ ደጃፎች ሦስት፡ በምዕራብ በሉ ፲፫
ደጃፎች ሦስት፡ በሰሜን በሉ ደጃፎች ሦስት፡ በደ
ቡብ በሉ ደጃፎች ሦስት ተጽፈዋል ። ሕዝ ፵፰፡ ፲፩ ።

የሀገሪቱም አርከን መሠረቶች ዓሥራ ሁለት ናቸው፡ ፲፬
የዓሥራ ሁለቱ የበጉ ሐዋርያት ስም በውስጣቸው
ተጽፏል ። ምዕ ፲፰፡ ፳ ። ማቴ ፲፡ ፪ ። ገላ ፪፡ ፱ ።
ያም ከኔ ጋር የሚነጋገረው መልአክ ያችን ሀገር ፲፭
ደጃፎችዋንና አርከኖችዋን የሚሰፍርበትን የወርቅ
ዘንግ ይዟል ። ዘካ ፪፡ ፩ ። ምዕ ፲፩፡ ፩ ።
ያችም ሀገር በወርዷ በቁመትዋ መጠን አራት መዓ ፲፮
ዝን ናት፡ ያችንም ሀገር በዚያው በወርቅ ዘንግ ሰፈ
ራት፡ መጠኗም ሺሕ ሁለት መቶ ሆነ፡ ርዝመቷ፡
ሞላልነትዋና ቁመትዋ ትክክል ነው ። ሕዝ ፵፰፡
፲፮ - ፲፯ ።
ከዚህ በኋላ የአርከኗ መጠን በሰው ክንድ መቶ አርባ ፲፯
አራት ሆነ፡ ይኸውም በመልአኩ ክንድ አንድ ክንድ
ነው ።
የዚያች ሀገር አርከን ቁፍ ያክንትና ኢያስጲድ በሚ ፲፰
ባል ዕንቍ ያጌጠ ነው፡ ሀገሪቱም በጥሩ ወርቅ የተ
ሠራች ትመስላለች ።
የሀገሪቷም ቅጽር መሠረት እንደ ሞ ብርሌ ፀዓዳ ፲፱
ነው፡ በከበረ ዕንቍ ሁሉ ያጌጠች ናት፡ መጀመር
ያዩቱ መሠረት ኢያስጲድ በሚባል ዕንቍ፡ ሁለተ
ኛዩቱም ሰንፔር በሚባል ዕንቍ፡ ሦስተኛዩቱም
ኬልቄዶን በሚባል ዕንቍ፡ አራተኛዩቱም መረግድ
በሚባል ዕንቍ ያጌጠች ናት ። ኢሳ ፶፬፡ ፲፩ - ፲፪ ።

፳ ወኃምስት በሰርዶንክስ፡ ወሳድስት በሰርድዮን፡ ወሳ
ብዕት በክርስቲሎቤ ፡ ወሳምንት በቢረሌ፡ ወታስዕት
በወራውሬ ፡ ወዓሥርት በክርስጵራስስ ፡ ወእንተ
ዐሥሩ ወአሐቲ በያክንት፡ ወእንተ ዐሥሩ ወክልኤ
በአሜቴስጢኖስ ።

፳፩ ወደ፻ደ፻ያቲሃኒ ዐሥሩ ወክልኤ በዐሥሩ ወክልኤ ባሕ
ርይ ወለለአሐቲ ደ፻ደ፻ አሐቲ ባሕርይ ፡ ወጽጕ ሀገራ
ከመ ወርቅ ንጹሕ ወያጸድል እንተ ውሥጣ ከመ
ማኀው ።
፳፪ ወኢርኢኩ ጽርሐ እንተ ከማሃ እስመ እግዚአብሔር
ዘኵሎ ይመልክ ውእቱ ጽርሓ ወበግዑ ።

፳፫ ወሀገራሰ ኢትፈቅድ ፀሐየ ወኢወርኀ ከመ ያብርሁ
ላቲ እስመ ብርሃነ እግዚአብሔር ያበርህ ላቲ ወማኅ
ቶታ ውእቱ በግዑ ።
፳፬ ወየሐውሩ አሕዛብ በብርሃነ ዚአሃ ፡ ወነገሥተ ምድ
ርኒ ያመጽኡ አምኃ እምክብሮሙ ውስቴታ ።
፳፭ ወኢይትዐፀው አናቅጺሃ መዐልተ ወሌሊተ እስመ
አልቦቱ ሌሊት ።
፳፮ ወአሕዛብኒ ያመጽኡ ክብሮሙ ወስብሐቲሆሙ ውስ
ቴታ ።
፳፯ ወኢይበውእ ውስቴታ ኵሉ ዘርኩስ ወዘይገብር
ግማኔ ወሐሰተ ወዘኢኮነ ጽሑፈ ውስተ መጽሐፈ
ሕይወት ዘበግዑ ።

ምዕራፍ ፳ወ፪ ፡

፩ ወአርአየኒ ፈለገ ዘማየ ሕይወት ፀዓዳ ከመ በረድ
ወይወፅእ እምነ መንበሩ ለእግዚአብሔር ወሥልጣነ
በግዑ ።
፪ ወይውኅዝ ውስተ ማእከለ መርኅበ ወእምለፌኒ
ውእቱ ፈለግ ወእምክሐሁኒ ዕፀ ሕይወት ወይገብር
ፍሬ ዐሥርተ ወክልኤተ ለለአሐዱ ወርኅ ወቈጽለ
ዕፀኒ ፈውስ ለሕይወተ አሕዛብ ።
፫ ወአልበ እንከ ርኩስ ወኢምንትኒ ፡ ወሀለወ ውስቴታ
መንበረ እግዚአብሔር ወበግዑ ወኢይከውን መዓት
ላዕለ አግብርቲሁ ለእግዚአብሔር እለ ያመልክዎ ።

፬ ወይሬእዩ ገጾ ወስሙ ውስተ ፍጽሞሙ ።

፭ ወአልበ እንከ ሌሊት ወኢይፈቅዱ ብርሃነ ማኅቶት
ወኢብርሃነ ፀሐይ እስመ እግዚአብሔር ያበርህ ላዕ
ሌሆሙ ወይነግሡ ለዓለመ ዓለም ።

አምስተኛዪቱ መሠረት ሰርዶንክስ በሚባል ዕንቍ ፡ ፳
ስድስተኛዪቱም ሰርድዮን በሚባል ዕንቍ ፡ ሰባተኛ
ዪቱም ክርስቲሎቤ በሚባል ዕንቍ ፡ ስምንተኛዪቱ
ቢረሌ በሚባል ዕንቍ ያጌጠች ናት ፡ ዘጠኛኛይቱም
ወራውሬ በሚባል ዕንቍ ፡ ዓሥረኛዪቱም ክርስጵ
ራስስ በሚባል ዕንቍ ፡ ዓሥራ አንደኛዪቱም ያክንት
በሚባል ዕንቍ ፡ ዓሥራ ሁለተኛዪቱም አሜቴስ
ጢኖስ በሚባል ዕንቍ ያጌጠች ናት ።
ዓሥራ ሁለቱ ደጃፎቿም በዓሥራ ሁለቱ አዕናቍ ፳፩
ያጌጡ ናቸው ፡ ለያንዳንዱ አርከን አንዳንድ ዕንቍ
አለበት ፡ የሀገሪቱም አደባባይ እንደ ጠራ ወርቅ
ነው ፡ ውስጢም እንደ ዕንቍ ያበራል ። ምዕ ፳፪ ፡ ፪ ።
እንደሷ ያለ አዳራሽ አላየሁም ፡ ሁሉን የሚገዛ እግ ፳፪
ዚአብሔር አዳራሿ ነውና ፡ በጉም አድሮባት ይኖ
ራልና ።
ሀገርነቷም ያበሩላት ዘንድ ፀሐይና ጨረቃን አት ፳፫
ሻም ፡ የእግዚአብሔር ብርሃን ያበራላታልና ፡ መብራ
ቷም በጉ ነውና ። ኢሳ ፷፬ ፡ ፳፫ ። ምዕ ፳፪ ፡ ፭ ።
አሕዛብ በብርሃኗ ይሄዳሉ የምድር ነገሥታትም ክብ ፳፬
ራቸውን ወደሷ ያመጣሉ ። ኢሳ ፷ ፡ ፫ - ፬ ።
በሮቿም ቀንና ሌሊት አይዘጉም ፡ ሌሊት የለባ ፳፭
ትምና ። ኢሳ ፷ ፡ ፳ ። ዘካ ፲፬ ፡ ፱ ። ራእ ዮሐ ፳፪ ፡ ፭ ።
አሕዛብ ዘውዳቸውንና ገንዘባቸውን ወደርሷ ያመ ፳፮
ጣሉ ።
ሐሰትን የሚናገር ፡ ኃጢአትን የሚሠራ ርኩስ ሁሉ ፳፯
አይገባባትም ፡ በበጉ ሕይወት መጽሐፍ ውስጥ ያል
ተጻፈም አይወርሳትም ። ኢሳ ፴፭ ፡ ፰ ። ዳን ፲፪ ፡ ፩ ።
ፊል ፬ ፡ ፫ ። ምዕ ፫ ፡ ፭ ። ፲፫ ፡ ፰ ። ፳ ፡ ፲፪ ።

ምዕራፍ ፳፪ ።

እንደ በረድ የጠራ የሕይወት ውኃ ያለበትን ወንዝ ፩
አሳየኝ ከእግዚአብሔር ዙፋንና ከበጉ ሥልጣን
ይወጣል ። መዝ ፵፮ ፡ ፬ ፡ ሕዝ ፵፯ ፩ ፡ ፲፪ ።
በአደባባይዋም መካከል ይፈሳል ከወዲህ ወንዝ ከወ ፪
ዲያም የሕይወት ዛፍ አለ ፡ በየአንዳንዱ ወር ዓሥ
ራ ሁለት ፍሬ ያፈራል የዛፉም ቅጠል ለአሕዛብ
ሰውነት መድኃኒት ነው ። ዘፍ ፡ ፪ ፱ ፡ ምዕ ፡ ፪ ፯ ።
ከዚያ በኋላ ግን ምንም ርኩስ አይገባባትም በውስ ፫
ጧም የእግዚአብሔርና የበጉ ዙፋን አለ፡ እግዚአብ
ሔርን በሚያመልኩት በለሚሎቹ ላይ ቍጣ አይሆ
ንም ። ዘካ ፡ ፲፬ ፲፩ ፡ ማቴ ፡ ፳፭ ፴፩ ፡ ምዕ ፡ ፳፩ ፬ ።
ፊቱን ያያሉ ስሙም በግንባራቸው ተጽፏል ። ፬
ማቴ ፡ ፭ ፰ ፡ ፩ ቆሮ ፡ ፲፫ ፲፪ ፡ ፩ ዮሐ ፡ ፫ ፪ ።
ከዚያ ወዲያ ጨለማ የለም ፡ የመብራትን ብርሃንና ፭
የፀሐይን ብርሃን አይሹም እግዚአብሔር ያበራላቸ
ዋልና ለዘለዓለሙም ነግሠው ይኖራሉ ። መዝ ፵፮
፱ ፡ መዝ ፡ ፹፬ ፲፩ ፡ ዳን ፡ ፯ ፲፰ ፡ ፳፮ ፡ ሮሜ ፭ ፲፯ ።

፮ ወይቤለኒ ዝንቱ ቃል ጽድቅ ወመሃይምን፤ እግዚእነ
ወእግዚአብሔር አምላከ መንፈሰ ነቢያት ዘፈነወ
መልአኮ ከመ ያርእዮሙ ለአግብርቲሁ ዘሀለወ ይኩን
ፍጡነ ።
፯ ወናሁ እመጽእ ፍጡነ ወብፁዕ ዘየዐቅብ ቃለ ትንቢ
ቶቱ ለዝንቱ መጽሐፍ ።
፰ ወአነ ዮሐንስ ዘርኢኩ ወዘሰማዕኩ ዘንተ ሰገድኩ
ቅድመ እገሪሁ ለውእቱ መልአክ ዘአርአየኒ ለዝንቱ፤
፱ ወይቤለኒ ኢትስግድ ሊተ ዑቅ ዮጊ ገብረ አጋእዝ
ቲከ አነ ወዘአኃዊከ ነቢያት ወዘእለ የዐቅቡ ቃለ
ዝንቱ መጽሐፍ ።
፲ ወአንተሰ ለእግዚአብሔር ስግድ ወኢትኅትም ቃለ
ትንብዮቱ ለዝንቱ መጽሐፍ እስመ በጽሐ ዘመኑ ።
፲፩ ወለዘገፍዐኒ ይገፍዕዎ እንከ፤ ወለዘረኰሶኒ ያረኵስዎ
እንከ፤ ወጻድቅ ለይጽደቅ፤ ወንጹሕኒ ለይንጻሕ ።
፲፪ ወናሁ እመጽእ ፍጡነ ወዕሤትየኒ ምስሌየ ውእቱ
ከመ እፍድዮ ለለአሐዱ ወአኩንኖ በከመ ምግባሩ ።

፲፫ አነ ውእቱ አልፋ ወኦ አነ ቀዳማዊ ወአነ ደኃራዊ
ርእስ ወማኅለቅት ።
፲፬ ብፁዓን እለ አንጽሑ አልባሲሆሙ ከመ ይኩን ሥል
ጣኖሙ ላዕለ ዕፀ ሕይወት ወይበውእዋ እንተ አናቅ
ጺሃ ለዛ ሀገር ።
፲፭ ወይወፅኡ አፍአ ኃምስቱ አከላብ እለ ሥራይ ወዘ
ማውያን ወቀታልያን ወእለ ያመልኩ ጣዖተ ወኵ
ሎሙ እለ ያፈቅሩ ግብረ ሐሰት ።

፲፮ አነ ኢየሱስ ፈነውኩ መልአክየ ያስምዕ ለክሙ
ዘንተ ለአብያተ ክርስቲያናት፤ አነ ውእቱ ሥርው
ዘእምዘመደ ዳዊት ኮከበ ብርሃን ጽባሓዊ ።
፲፯ ወመንፈስ ቅዱስ ዘመርዓት ወይቤሉ ለይምጻእ ወዘ
ጸምአኒ ለይምጻእ ወዘይፈቅድ ለይንሣእ ማየ ሕይ
ወት በከንቱ ።

፲፰ ወአነ ስምዑ ለኵሉ ዘይሰምዕ ቃለ ዝንቱ መጽሐፍ
እመ ወሰከ ዲቤሁ ይዌስክ እግዚአብሔር ላዕሌሁ
መቅሠፍተ ዘጽሑፍ ውስተ ዝንቱ መጽሐፍ ።
፲፱ ወእመኒ አሰሰለ እምውስተ ቃለ ዝንቱ መጽሐፍ
ያሴስል እግዚአብሔር ክፍሎ እምዕፀ ሕይወት ወእ
ምነ ሀገር ቅድስት ዘጽሑፍ ውስተ ዝንቱ መጽሐፍ ።
፳ ወይብል ዘሰምዐ ዘንተ እወ እመጽእ ፍጡነ፤ አሜን
ነዓ እግዚእየ ኢየሱስ ።
፳፩ ጸጋሁ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ምስለ ኵልክሙ
አሜን ።

በዝየ ተፈጸመ ራእየ ዮሐንስ አቡቀለምሲስ፤ ዘውእቱ
ብሂል ዘርእየ በሕይወቱ ራእየ ።
ወስብሐት ለእግዚአብሔር ፤ አሜን ።

ያው የታመነ እውነተኛ ቃል ፈጣሪያችን እግዚአብ ፮
ሔር ፈጥኖ ይሆን ዘንድ ያለውን ለባለሟሎቹ ይገል
ጥላቸው ዘንድ መልአኩን የላከ የነቢያት መንፈስ ።
ዕብ፤ ፩ ፩፤ ምሳ፤ ፩ ፩ ።
እነሆ ፈጥኜ እመጣለሁ የዚህንም መጽሐፍ የትንቢ ፯
ቱንም ቃል የሚጠብቅ ሰው የተመሰገነ ነው አለኝ።
ይህን ያየሁ የሰማሁ እኔ ዮሐንስ ይህን ለገለጠልኝ ፰
መልአክ ከእግሩ በታች ሰገድሁ ። ምዕ፤ ፲፱ ፲ ።
እንግዲህ ለኔ እንዳትሰግድ ዕወቅ፤ እኔ የጌቶችህ አገ ፱
ልጋይ ነኝና የወንድሞችህ የነቢያትና የዚህን መጽ
ሐፍ ቃል የሚጠብቁ ሰዎች ባልደረባ ነኝ ።
አንተስ ለእግዚአብሔር ስገድ አለኝ፤ የዚህንም መጽ ፲
ሐፍ የትንቢቱን ቃል አትሠውር ዘመኑ ደርሷልና ።
እንግዲህ የበደለውን ይበድሉታል ያሳደፈውንም ያሳ ፲፩
ድፉታል፤ ጻድቁም ይጽደቅ፤ ንጹሑም ንጹሕ ይሁን።
እነሆ ፈጥኜ እመጣለሁ ለየአንዳንዱም እንደየሥ ፲፪
ራው ፈርጄ ብድሩን እከፍለው ዘንድ የምሰጠው
ዋጋ ከኔ ጋር ነው ። ቊ፤ ፲፯፤ ኢሳ፤ ፵ ፲ ።
አልፋ፤ ኦ የምባል ፊት የነበርሁ ኋላም የምኖር ጥን ፲፫
ትና ፍጻሜ የምሆን እኔ ነኝ። ኢሳ፤ ፵፬ ፮ ።
ሥልጣናቸው በዕፀ ሕይወት ላይ ይሆን ዘንድ ልብ ፲፬
ሳቸውን ያነጹ ወደዚያች ሀገርም በበሮቿ የሚገቡ
የተመሰገኑ ናቸው ። ዳን፤ ፲፪ ፲፪፤ ምዕ፤ ፲፫ ፮ ።
አምስቱ ውሾች ግን ከዚያች ሀገር ወጥተው ይኼ ፲፭
ዳሉ እሊህም ሥራይን የሚያደርጉ፤ ሌሰኞች፤ ነፍሰ
ገዳዮች ጣዖትን የሚያመልኩና የሐሰትን ሥራ የሚ
ወዱት ሁሉ ናቸው ። ምዕ፤ ፳፩ ፳፯፤ ፩ ቆሮ፤ ፮ ፱ ፲።
ለእናንተ ለአብያተ ክርስቲያናት ይህን ያሰማችሁ ፲፮
ዘንድ እኔ ኢየሱስ መልአክተኛዬን ላክሁ፤ ከዳዊት
ወገን የምሆን ሥሩ የማበራ የአጥቢያ ኮከብ እኔ ነኝ።
በምእመናን አድሮ የሚኖር መንፈስ ቅዱስ ሕይወቱ ፲፯
የሚሆን ምእመናንም ይምጣ ያሉኝ እኔ ነኝ፤ የተጠ
ማም መጥቶ የሚሻውን የሕይወት ውኃ ያለ ዋጋ
ይጠጣ ። ኢሳ፤ ፶፭ ፩፤ ዮሐ፤ ፬ ፲፬፤ ዮሐ፤ ፯ ፴፯ ።
የዚህን መጽሐፍ ቃል ሰምቶ በዚህ ላይ ቢጨምር ፲፰
በዚህ መጽሐፍ ውስጥ የተጻፈውን መቅሠፍት እግ
ዚአብሔር እንዲጨምርበት እኔ ምስክር ነኝ ።
ከዚህም መጽሐፍ ቃል ቢያጎድል ከዕፀ ሕይወትና ፲፱
በዚሁ መጽሐፍ ውስጥ ከተጻፈችው ከቅድስት ሀገር
እግዚአብሔር ዕድሉን ያጎድልበታል። ዘፀ፤ ፴፪ ፴፫።
ይህንንም የሰማ እውነት ነው ይበል በእውነት ፈጥኜ ፳
እመጣለሁና ኢየሱስ ጌታዬ ና ይበል ። ዕብ፤ ፲ ፳፫።
የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ጸጋው ከሁላችሁ ጋር ፳፩
ይሁን፤ አሜን ።

አቡቀለምሲስ ዮሐንስ ያየው ራእይ ተፈጸመ፤ ይኸውም
በሕይወቱ ያየው ራእይ ማለት ነው ።
ለእግዚአብሔር ምስጋና ይሁን፤ አሜን ።

# መጽሐፈ ዲድስቅልያ

## ዘአበዊነ ሐዋርያት



አሳታሚ፡- ትንሣኤ ማሳተሚያ ድርጅት

፲፱፻፸ ዓ.ም.

## መ ግለ ጫ

ንሕነሰኬ ኢንክል ከቢቶቶ ለዝንቱ ነገር"
እኛስ ይህንን ነገር ልንሠውረው አንችልም።
(ግብረ ሐዋርያት ፬ ፡ ፳)

በብሂለ አዖ ፡ "በቃል ያለ ይረሳል፣ በመጽሐፍ ያለ ይወረሳል" እንደተባለው በየዐረፍተ ዘመኑ በልብ የታሰበውን፣ በቃል የተነገረውን፣ በተግባር የተፈጸመውን፣ ማንኛውንም ክንውን በጽሑፍ አስፍሮ፣ የተጻፈውንም በክብር ጠብቆና አቆይቶ ለትውልድ ማስተላለፍና በየዐረፍተ ዘመኑ ከሚነሳው ትውልድ ሁሉ የሚጠበቅ ታሪካዊ ግዴታ ነው።

በመሆኑም ጥንታዊትና ታሪካዊት፣ እንዲሁም ብሔራዊት የሆነችው የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያናችን ከተቀበለቻቸው አምላካውያት ሰማንያ ወአሐዱ ቅዱሳት መጻሕፍት ውስጥ ስምንቱ የሕግና የሥርዓት መጻሕፍት ናቸው።

<u>በዝርዝር ሲገለጹም</u> :-

- ሥርዓተ ጽዮን ፤
- ትእዛዝ፤
- ግጽው፤
- አብጥሊስ፤
- ፩ኛ መጽሐፈ ኪዳን፤
- ፪ኛ መጽሐፈ ኪዳን፤
- ቀሌምንጦስ፤
- ዲድስቅልያ

በመባል ይታወቀቀሉ።

ሰዋቢነት የሚቀርበውም "ለመጻሕፍተ ቀኖናትሰ ቀዳሚሆሙ ቀኖና፣ "ዘሠርዕዋ ሐዋርያት። ወእሙንቱ እንዘ ጉቡአን በጽርሐ ጽዮን፣ እምድኅረ ዕርገት፣ ወርደተ መንፈስ ቅዱስ ላዕሌሆሙ ወእምቅድመ ይዘረዉ በእንተ ስብከት" የሚለው ገጸ ንባብ ሲሆን፣ ትርጓሜውም የቀኖና መጻሕፍት መጀመሪያቸው፣ ሐዋርያት የሠሩዋት ናት። እነርሱም ከዕርገትና መንፈስ ቅዱስ በእነርሱ ላይ ከወረደ በኋላ ፣ ለስብከተ ወንጌል ከመበተናቸው አስቀድሞ በጽርሐ ጽዮን ተሰብስበው ሳሉ የሠሩዋት ናት የሚለው ነው። (መቅድመ ፍትሐ ነገሥት ገጽ ፲፪ ፓራግራፍ ፫።)

ሐዋርያው ቅዱስ ጳውሎስም "አኃዊነ! ንኤዝዘክሙ በስመ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ፣ ተገሐሥዎሙ ለኵሎሙ ቢጽ እለ የሐውሩ በትምይንት፣ ወአኮ በሥርዐት ዘሠራዕናሆሙ" 2ኛ ተሰ 3:6)

ወንድሞቻችን! በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ስም እናዝዛችኋለን፤ በሠራንላቸው ሥርዐት ያይደለ በተንኮል የሚሔዱትን ሰዎች ሁሉ ተለዩአቸው። በሚለው ቃል ሐዋርያ መሠረት ቤተ ክርስቲያን ቤተሰቦችዋን፣የእምነት ተከታዮችዋ፣ ምእመናንን የምታስተዳድርባቸው የሕግና የሥርዐት መጻሕፍት ናቸው።

ከስምንቱ የሥርዐት መጻሕፍት አንዱ "ዲድስቅልያ" የተሰኘው የሥርዓት መጽሐፍ ነው። ዲድስቅልያ ማለትም ፣ ቃሉ የጽርእ ቃል ሲሆን ትርጓሜውም ትምህርት ማለት ሆኖ፣ ከላይ እንደ ተገለጸው ቅዱሳን ሐዋርያት ከሐዲስ ኪዳን ለትምህርት አውጣጥተው ያዘጋጁት ነው።

"መቅድመ መሐርምሙ ለውሉድክሙ መጽሐፈ ሲራክ ወሰሎሞን፣ ወመዝሙረ ዳዊት ወዲድስቅልያ" እንደተባለው የሥርዐት መጽሐፍ ብቻ ሳይሆን ለትምህርተ ሕፃናትም ጠቃሚ እና አስፈላጊም ነው። ዲድስቅልያ የተሰኘው ይህ የሥርዐት መጽሐፍ በ፵፫ አናቅጽ የተከፈለ ሲሆን፣ ከቀድሞ የቤተ ክርስቲያን አባቶች ከተላለፉልን የሥርዓት መጻሕፍት አንዱ ስለሆነ ጠቢቡ ሰሎሞን በመጽሐፈ መክብብ ፫፡፩-፩ ላይ "ለ ለኵሉ ዘመን፣ ወለ ጊዜ ለኵሉ ምግባር ዘታሕተ ፀሐይ" ለሁሉ ዘመን አለው፤ ከፀሐይ በታችም ለሆነ ነገር ሁሉ ጊዜ አለው፣ በማለት እንደተናገረው፣ ቀደም ሲል በቁም ጽሕፈት ተጽፎ፣ በቤተ መጻሕፍት ወመዘክር በክብር ተጠብቆ፣ አንድ ለራሱ ሆኖ ተቀምጦ የነበረው መጽሐፈ ዲድስቅልያ ለመላው አብያተ ክርስቲያናት፣ ለትምህርትና ለምርምር ይበጅ ዘንድ፣ በማሳተሚያ ድርጅታችን ተዘጋጅቶ፣ በሊቃውንት ጉባኤ ተመርምሮ፣ ታትሞ እንዲሰራጭ ማድረጋችንን ስናበሥር መንፈሳዊ ደስታ ይሰማናል።

ሐዋርያት የሰማርያን ሰዎች ባስ ተማሩ ጊዜ ሲሞን መሠርይ እጃ ቸውን በጫኑበት ላይ፣ መንፈስ ቅዱስ ሲወርድ፣ ተአምራት ሲደ ረግ፣ ድውያን ሲፈወሱ አይቶ ይህ ተአምራታቸው የሥራይ መስሎት እኔም እጄን በጫንኩበት መንፈስ ቅዱስ እንዲአድር፣ተአም ራት እንዲደረግልኝ አድርጉኝ ብሎ በሥራይ የሰበሰበውን ብዙ ወርቅ ብር አምጥቶ ለሐዋርያት ሰጣ ቸው፤ ጴጥሮስ ወርቅከ ወብሩርከ ይኩንክ ለከ ለሕርትምና፤ ወርቅህ ብርህ ላንተ ለጥፋትህ ይሁንኽ፣ ይመስለከኑ ዘበወርቅ ትሣየጦ ለጸጋ እግዚአብሔር ፣ አንዱን አካል ወልድን ይሁዳ ሸጠው፤ እኛ ደግሞ አንዱን አካል መንፈስ ቅዱስን የምን ሸጥልህ በወርቅ የምትገዛው ይመስልሃልን፣ አል ብከ ክፍል ውስተዝ ነገር ፣ መንፈስ ቅዱስን ማሳደር ፣ አን ድም ከኛ ጋር እድል ፈንታ ጽዋ ተርታ የለህም፣ በጽኑ ክህደት ተይዘህ አይሃለሁና አለው፤ እሱም ይህ ሁሉ እንዳይደረግብኝ ጸልዩልኝ አለ።

ከዚህ የማይሆንለት ቢሆን አንጾ ኪያ ወርዶ ያስት ጀመረ፣ ለጴጥሮስ ደቀ መዛሙርትህን አሳተ ብለው ነገሩት ፣ ዮሐንስን አስከትሎ አንጾኪያ ወረደ፣ ሲሞን መከራከር የማይቻለው ቢሆን ሮም ወረደ ፣ ከዚያም ሄዶ አልተወም፣ ያስታል ብለው ነገሩት፣

ጴጥሮስ ዮሐንስን አስከትሎ ወርዶ ቅብውን በአንቀጸ ሮም አግኝተው ፈውሰውት ገብተዋል ። ተአምራትስ ይሕታ (ይህ ነው) ብለው ሕዝቡ ወደ እነሱ ተሳቡ፣ ለመሥዋዕት የቀረበ ላም ነበር ሹክ፣ ሹክ ቢለው ከሁለት ተከ ፈለ ፣ ከሚዛን ቢአገቡት ትክክል ሁኗል፣ ሚዛኑ የዓይን ነው። ተአምራትስ ይሕታ (ይህ ነው) ብለው ወደ ሲሞን ተሳቡ፣ ቅዱስ ጴጥሮስ ቢባርከው ተነሳ፣ ጠርተህ አምጣው አለው በቃል ሰብአዊ ጠርቶ እያዳፋ እያጋፋ አመጣው ፤ ተአምራትስ ይሕታ (ይህ ነው) ብለው ወደ ሐዋርያት ተሳቡ፣ በሬ አስነሥቶ ማስቀ ባጠር ቁም ነገር ነውን ብሎ አጋንንትን በምስሐቡ ስቦ ያንተ ሀብት ይህ ነው፣ አንተን ቅስና፣ አንተን ዲቁና ሹሜሃለሁ ብሎ ዐረግሁ አለ፣



ዮሐንስ ቅዱስ ጴጥሮስን አበ ዓለም ዝም ትላለህን አለው፣ ተወው በእምር ከፍ ይበል አለው፣ በእምር ከፍ ሲል ቢያማትብበት አጋንንት ጥለውት ሸሹ፣ ወድቆ ተንቆጫቁጮ ሙቷል።

ከዚያ የነበሩት የእርሱ ደቀ መዛ ሙርትም ብዙ ክህደትና ኑፋቄ አፍልቀዋል።

በዚህ ምክንያት አሥራ ሁለቱ ሐዋርያት፣ ሰባ ሁለቱ አርድዕት፣ ንዋይ ኅሩይ ጳውሎስ፣ ያዕቆብ እኁሁ ለእግዚእነ ሁነው በኢየሩ ሳሌም ተሰብስበው አርባ ሦስት አንቀጽ፣ዲድስቅልያ ተናግረዋል። ይህንኑም ጌታ ባረገ በሃያ ሁለት ዓመት በፊልጵስዩስ ሕንፀተ ቤተ ክርስቲያንን ካሳያቸው፣ ሥርዓተ ቤተ ክርስቲያንን ካስተማራቸው በኋላ፣ እንደ አንድ ቃል ተናጋሪ፣ እንደአንድ ልብ መካሪ ሁነው ወስ ነው ጽፈው ለቀሌምንጦስ ሰጥተ ውታል፣ ከዚያ አንሥቶ በመምህ ራን ቃል ሲነገር ከዚህ ደርሷል።

ይኸውም ለኛ ምክር እዝናት ሲሆን ተጽፎልናል፣

መጽሐፉ ባዘዘው ሥርዓት ብንጸና ተስፋችንን ካለኝታችን ፍጻሜ ከኢየሱስ ክርስቶስ እናገኝ ዘንድ፣ ወኵሉ ዘተጽሕፈ ለተግሣጸ ዚአነ ተጽሕፈ ፣ ከመ በትዕግሥትነ ወበተወክሎተ መጻሕፍት ንርከብ ተስፋነ እንዲል፣

ልመናቸው በረከታቸው በወዳ ጃቸው በርእሰ ሊቃነ ጳጳሳት፣ ወፓትርያርክ አባ ጳውሎስ ይደ ርና ንጹሓን ክቡራን የሚሆኑ አባቶች ሐዋርያት ያስተማሩት የዲ ድስቅልያ ትምህርት ይህ ነው።

ማውጫ



ማውጫ

ማውጫ



ማውጫ

## ማውጫ

| አንቀጽ | ገጽ | አንቀጽ | ገጽ |
|---|---|---|---|
| አንቀጽ ፴፪. በእንተ ዘከመ አብአ ሰይጣን ፍልጠተ፤ | ገጽ ፪፻፺፪ | አንቀጽ ፴፪. ሰይጣን በቤተክርስቲያን ውስጥ ክርክርንና መለያየትን ስለማስገባቱ፤ | ገጽ ፪፻፺፪ |
| አንቀጽ ፴፫. በእንተ ርትዕት ሃይማኖት ወቅድስት ሥላሴ፤ | ገጽ ፪፻፺፰ | አንቀጽ ፴፫. ስለ ቀናች ሃይማኖትና ስለ ቅድስት ሥላሴ፤ | ገጽ ፪፻፺፰ |
| አንቀጽ ፴፬. በእንተ ከመ መፍትው ይጸልዩ ወይስአሉ ወይዘምሩ ላዕለ እለ አዕረፉ፤ | ገጽ ፫፻፯ | አንቀጽ ፴፬. ስለሞቱ ሰዎች ይጸልዩና ይዘምሩ ዘንድ እንዲገባ፤ | ገጽ ፫፻፯ |
| አንቀጽ ፴፭. በእንተ ፃማ ወአኮቴት፤ | ገጽ ፫፻፲ | አንቀጽ ፴፭. ስለ መንፈሳዊ ምስጋናና ድካም፤ | ገጽ ፫፻፲ |
| አንቀጽ ፴፮. በእንተ ሜሮን፤ | ገጽ ፫፻፲፰ | አንቀጽ ፴፮. ስለ ሜሮን፤ | ገጽ ፫፻፲፰ |
| አንቀጽ ፴፯. በእንተ ቅኔ ሠራዊት መንፈሳውያን፤ | ገጽ ፫፻፳፬ | አንቀጽ ፴፯. ስለ መንፈሳውያን መላእክት አገልግሎት፤ | ገጽ ፫፻፳፬ |
| አንቀጽ ፴፰.በእንተ ከመ መፍትው ናዕርፍ ሰንበታተ፤ | ገጽ ፫፻፳፯ | አንቀጽ ፴፰. በሰንበቶች ቀን ማረፍ እንዲገባ፤ | ገጽ ፫፻፳፯ |
| አንቀጽ ፴፱. በእንተ ንዑሰ ክርስቲያን፤ | ገጽ ፫፻፴፭ | አንቀጽ ፴፱. ይጠመቁ ዘንድ ስለ ሚወለዱ ንዑስ ክርስቲያን፤ | ገጽ ፫፻፴፭ |
| አንቀጽ ፵. በእንተ ጸሎት ዘይትነበብ ዲበ ማይ፤ | ገጽ ፫፻፴፱ | አንቀጽ ፵. በክርስትና ጊዜ በመጠመቂያ ውሀ ላይ የሚጸለይ ጸሎት፤ | ገጽ ፫፻፴፱ |

## ማውጫ

| አንቀጽ | ገጽ | አንቀጽ | ገጽ |
|---|---|---|---|
| አንቀጽ ፵፩. በእንተ ጸሎት ላዕለ ሜሮን፤ | ገጽ ፫፻፵፩ | አንቀጽ ፵፩. በሜሮን ላይ ስለ ሚጸለይ ጸሎት፤ | ገጽ ፫፻፵፩ |
| አንቀጽ ፵፪. በእንተ ዘከመ ይጸልዩ ዘንተ ጸሎተ ሐዲሳን እለ ተጠምቁ፤ | ገጽ ፫፻፵፩ | አንቀጽ ፵፪. አዲስ አማንያን ሲጠመቁ ስለሚጸልዩት ጸሎት | ገጽ ፫፻፵፩ |
| አንቀጽ ፵፫. በእንተ ኤጲስ ቆጶሳት እለ ተሠይሙ በኀበ ሐዋርያት፤ | ገጽ ፫፻፵፪ | አንቀጽ ፵፫. በሐዋርያት ስለተሾሙ ኤጲስ ቆጶሳት የሚናገር፤ | ገጽ ፫፻፵፪ |

## አንቀጽ ፩

ዲድስቅልያ ዘውእቱ ትምህርት ዘአበው ቅዱሳን ሐዋርያት፤ ጸሎቶሙ ወበረከቶሙ የሀሉ ምስሌነ ለዓለመ ዓለም አሜን::

በስመ እግዚአብሔር አብ አኃዜ ኵሉ ወወልዱ ዋሕድ ኢየሱስ ክርስቶስ ወጰራቅሊጦስ መንፈስ ቅዱስ ::

፩ ንሕነ እሙንቱ ዐሠርቱ ወ፪ቱ ሐዋርያት ላእካኒሁ ለወልድ ዋሕድ ኢየሱስ ክርስቶስ ተጋቢአነ አሐተኔ በኢየሩሳሌም ሀገሩ ለንጉሥ ዐቢይ፣ወምስሌነ እኁነ ጳውሎስ ኄር ወንጹሕ፣ ሐዋርያሆሙ ለኵሎሙ አሕዛብ፣ ወያዕቆብ እኁሁ ለእግዚእነ ዘውእቱ ኤጲስ ቆጶስ ለዛቲ ሀገር ኢየሩሳሌም ሠራዕናሃ ለዛቲ ርትዕት ትምህርት::

፪. ወአዘዝነ ከመዝ መዓርገ ሢመታት ለቤተ ክርስቲያን በአርአያ ዘበሰማያት::

፫. ወንሕነ ንጌሥጸክሙ ከመ ይንበር ኵሉ ለለ አሐዱ አሐዱ እምኔክሙ ውስተ ዘተጸውዐ እምኀበ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ።

## አንቀጽ ፩

የቅዱሳን አበው ሐዋርያት ትምህርት ዲድስቅልያ፤ ጸሎታቸውና በረከታቸው ከእኛ ጋር ይኑር::

ሁሉን በያዘ በእግዚአብሔር አብ በአንድ ልጁ በኢየሱስ ክርስቶስ ናዛዚ በሚሆን በመንፈስ ቅዱስ ስም::

፩ የአንድያ ልጅ የኢየሱስ ክርስቶስ አገልጋዮች እኛ ዐሥራ ሁለቱ ሐዋርያት በታላቁ ንጉሥ ከተማ በኢየሩሳሌም በአንድነት ተሰብስበን ከእኛም ጋር የአሕዛብ ሁሉ ሐዋርያቸው ደግና ንጹሕ ወንድማችን ጳውሎስ፤ የዚችው ከተማ የኢየሩሳሌም ኤጲስ ቆጶስ የጌታችን ወንድም ያዕቆብም ከእኛ ጋር ሆነው ይህችን የቀናች ትምህርት ሠራናት::

፪. የቤተ ክርስቲያንን የሹመቶች መዓርግ በሰማያት ባለው አምሳል እንደዚህ አዘዝን::

፫. ከእናንተም ሁሉ እያንዳንዱ ከጌታችን ከኢየሱስ ክርስቶስ ዘንድ በተጠራበት ጸንቶ ይኖር ዘንድ እኛ እንመክራችኋለን::

፱. ኤጲስቆጶስ በአምሳለ ኖላዊ፤ ወቀሳውስት በአምሳለ መገሥጻን፤ ወዲያቆናት በአርአያ ላእካን ፤ ወንፍቀ ዲያቆናትሂ ናሁ ከመ ረዳእያን፤ ወአናጕንስጢሳውያን ከመ አንባብያን በጥይቅና፤ ወአብስሊድሳውያን ከመ መዘምራን፤ ወባዕዳንሰ ከመ እለ ያጸምዑ ቃለ ወንጌል::

፲. ወዓዲ ይለብዉ ነገረ ተግሣጽ፤ እስመ ከመዝ ረከብነ ወሠራዕነ ሕገ ለቤተ ክርስቲያን ወጸሐፍነ ዘንተ መጽሐፈ ተግሣጽ ወፈነውነ ምስለ ቀሌምንጦስ እኁነ ላእክ ለዝንቱ ዓለም ከመ ይሑሩ በትእዛዝ አብያተ ክርስቲያናት እለ መትሐተ ሰማይ ወይለብዉ ጥዩቀ ፤ ከመ ሶበ ሰምዑ ዘንተ ትእዛዘ ዘጽሑፍ ውስቴቱ፤ ወይርከቡ ሕይወተ ዘለዓለም ክብረ ወስብሐተ በኀበ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ዘጸገወነ ዘንተ ምሥጢረ ዘእምኀቤሁ::

፲፩. ወእለ ኢየዐቅቡ ሕጎ ይወድቁ ውስተ እሳት ዘኢይጠፍእ፤ ወዓዲ ይከውን ምንባሮሙ ውስተ ገሃነም በከመ ጽሑፍ እስከ ለዓለም::[፩]

፩. ማቴ. ፳፭፤ ፵፮

፱. ኤጲስቆጶሱ እንደ ጠባቂ ነው፤ ቀሳውስትም እንደ መምህራን ናቸው፤ ዲያቆናትም እንደ አገልጋዮች ናቸው፤ ንፍቀ ዲያቆናትም እነሆ እንደ ረዳቶች ናቸው፤ አናጕንስጢሳውያንም በማስተዋል እንደ አንባብያን ናቸው፤ አብስሊድሳውያንም እንደ መዘምራን ናቸው፤ ሌሎች ግን የወንጌልን ቃል እንደሚያዳምጡ ናቸው::

፲. ዳግመኛም የትምህርቱን ቃል ያስተውሉ፤ እንደዚህ ስላገኘነው ለቤተ ክርስቲያን ሕግ አድርገን ሠራን፤ ይህንም የምክር መጽሐፍ ጽፈን የዓለም መምህር በሆነው በወንድማችን በቀሌምንጦስ እጅ ላክን፤ ከሰማይ በታች ያሉ አብያተ ክርስቲያናት በትእዛዝ ፀንተው ይኖሩ ዘንድ፤ በውስጡ የተጻፈውንም ይህንን ትእዛዝ በሰሙ ጊዜ በእርግጥ ያስተውሉ ዘንድ፤ ይህንም ምሥጢር ከራሱ በሰጠን በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ዘንድ የዘለዓለም ሕይወትን ክብርንና ምስጋናንም ያገኙ ዘንድ::

፲፩. ሕጉን የማይጠብቁ ግን በማይጠፋ እሳት ይወድቃሉ ፤ ዳግመኛም እንደተጻፈ መኖሪያቸው እስከ ዘለዓለም ድረስ በገሃነም ውስጥ ይሆናል::



፲፪ ወሐዋርያትሰ ወቀሲሳን ወኵሎሙ አሕዛብ እለ አምኑ በስመ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወገብሩ ጽድቀ ወሰላመ ይረክቡ ሣህለ ወምሕረተ በኀበ እግዚአብሔር አብ አኃዜ ኵሉ ዓለም ወወልዱ ኢየሱስ ክርስቶስ ፤ ወይበጽሑ ውስተ አእምሮ ዚአሁ በቅድስት ቤተ ክርስቲያኑ ለእግዚአብሔር ፤ ወእለሰ ተቀንዩ ሎቱ ይከውኑ ዐፀደ ወይን ንጹሐ ወኅሩየ ወይረክቡ ሕይወተ ዘለዓለም በዛቲ አሚን ወመዊአ በመንፈስ ቅዱስ፤ ወይጸንዑ በኀይለ ኢየሱስ ክርስቶስ፤ ወበአሚነ ዚአሁ ዘቤዘዎሙ በንዝኀተ ደሙ ቅዱስ ወክቡር፤ ወጸገዎሙ ስብሐተ፤ ከመ ይጸውዕዎ ለአኃዜ ዙሉ ከመ ይኩኖሙ አቡሆሙ ወአምላኮሙ ወዐርኮሙ ወመዋርስቲሆሙ ወይረስዮሙ ሱታፌሁ ለወልድ ቅዱስ::

፲፫.ስምዑ ተግሣጸ ቅዱሰ እለ ትትዌከፉ ቃለ ወንጌል በትእዛዘ መድኀኒነ ፤ ወዜናሁ ዘምሉዕ ስብሐተ ኦ ደቂቀ እግዚአብሔር ዕቀቡ ትእዛዛቲሁ ወግበሩ ሥምረቶ::

፲፪. ነገር ግን ሐዋርያትና ቀሳውስት በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ስም ያመኑ አሕዛብም ሁሉ ጽድቅንና ሰላምን ያደረጉም ሁሉን በያዘ በእግዚአብሔር አብና በልጁ በኢየሱስ ክርስቶስ ዘንድ ይቅርታንና ቸርነትን ያገኛሉ፤ በቅድስት የእግዚአብሔር ቤተ ክርስቲያንም እርሱን ወደ ማወቅ ይደርሳሉ፤ ለእርሱ ያገለገሉም ንጹሕና የተመረጠ የወይን ቦታ ይሆናሉ፤ በዚችም እምነት የዘለዓለምን ሕይወት ያገኛሉ፤ በመንፈስ ቅዱስም ድል መንሳትን ያገኛሉ፤ በኢየሱስ ክርስቶስም ኃይል ይጸናሉ፤ በቅዱስና ክቡር ደሙ ፈሳሽነት የዋጃቸው እርሱን በማመንም ይጸናሉ፤ አባታቸውና አምላካቸው ወዳጃቸውና ርስታቸው ይሆናቸው ዘንድ፤ የቅዱስ ልጁም ተባባሪዎች ያደርጋቸው ዘንድ ሁሉን የያዘውን እንዲጠሩ ክብር ሰጣቸው::

፲፫. በመድኀኒታችን ትእዛዝ የወንጌልን ቃል የምትቀበሉ ቅዱሱን ትምህርትና ክብርን የተመላውን ወንጌሉን ስሙ ፤ የእግዚአብሔር ልጆች ሆይ! ትእዛዛቱን ጠብቁ፤ ፈቃዱንም አድርጉ::

፱. ወእመሰ ቦ ዘየኀሥሥ ይት ልዋ ለኀጢአት ወይገብር ኵሎ ዘኢያሠምሮ ለእግዚአብሔር ፤ ውእቱኬ ይትኌለቍ ምስለ እለ ዐለዉ ሕጎ ወትእዛዞ፡፡

፲ ወይእዜኒ እብለክሙ ፤ ረኀቁ እምዐመፃ ወትዕግልት ፤ ወኢት ፍቅዱ ለርእዕክሙ ነሢአ ክፍል ዘየዐቢ ፤ ወለቢጽክሙ ኅዳጠ ፤ እስመ ጽሑፍ ውስተ ሕግ ዘይብል «ኢትፍቱ ብእሲተ ካል እከ ኢገራህቶ ወኢገብሮ ወኢ አመቶ ኢላሕሞ ወኢአድጎ ወኢ ምንተኒ ኵሎ ንዋዮ ለእኁከ»[፪] ወኵሉ ዘይመስሎ ለዝንቱ ዝሙት ውእቱ፡፡

፲፩. ወእመሰ ቦ ዘይፈቅድ ይግ በር ከመዝ በፍትወተ ልቡ ይከውን ርኁቀ እምእግዚእነ ኢየ ሱስ ክርስቶስ እግዚአብሔር ዘሎቱ ስብሐት ምስለ አቡሁ ወመንፈስ ቅዱስ ለዓለመ ዓለም አሜን፡፡

፲፪.እስመይሜህረነ፤ ወያሌብወነ፤ ወያጸንዐነ በመንፈስ ቅዱስ ከመ ንፈጽም ሕገ ዘጽሑፍ ውስቴቱ፣ ዘይብል ኢትዘምዉ፡፡

፪. ዘፀ. ፳ ፡ ፲፯

፱. ኀጢአትን ይከተል ዘንድ የሚ ፈልግ፣እግዚአብሔርንም ደስ የማ ያሰኘውን ሁሉ የሚሠራ ቢኖር ግን እርሱ ሕጉንና ትእዛዙን ከለ ወጡ ሰዎች ጋር ይቈጠራል፡፡

፲.አሁንም እላችኋለሁ፤ ከዐመፅና ከቅሚያ ራቁ፤ ለራሳችሁ የሚበል ጠውን ክፍል መውሰድን፣ለወን ድሞቻችሁ ግን ጥቂት መስጠ ትን አትውደዱ፤ በሕግ እንዲህ የሚል ተጽፎአልና « የባልንጀራ ህን ሚስቱን፣ እርሻውን፤ ወንድ ባሪያውን ፤ ሴት ባሪያውን፤ በሬ ውንም፤ አህያውንም ፤ ማንኛው ንም የወንድምህን ገንዘብ ሁሉ ምንም አትመኝ» ይህንም የመ ሰለው ሁሉ ዝሙት ነው፡፡

፲፩. በልቡ ምኞት እንደዚህ ይሠራ ዘንድ የሚወድ ቢኖር ግን ከአባቱና ከመንፈስ ቅዱስ ጋር ለዘለዓለም ክብር ምስጋና ከሚገባው ከጌታችን ከእግዚአብሔር ኢየሱስ ክር ስቶስ የራቀ ይሆናል አሜን፡፡

፲፪. በመንፈስ ቅዱስ ያስተምረ ናልና እንድናውቅም ያደርገናልና፤ ያጸናናልና አትሰስኑ የሚል በውስጡ የተጻፈበትንም ሕግ እንፈጽም ዘንድ፡፡



፲፫.« ወአንሰ እብለክሙ ኵሉ ዘር እያ ለብእሲት ወፈተዋ ወድአ ዘመወ ባቲ በልቡ[፫]» ፡፡

፲፬.ወዓዲ ዘይፈቅድ ይግበር ከመዝ ይትኌነን ምስለ ዘማውያን፡፡

፲፭. ወናሁ ከመ ውእቱ ዘይኄሊ በልቡ ወይፈቱ ይንሣእ በዐመፃ ላህሞ፣አው አድጎ፣ አው ገራህቶ፣ ወያሐዩ እንዘ ከመዝ ይገብር ይትኌለቍ ምስለ ዘማውያን እስመ ይቤ በነቢይ አሌ ሎሙ ለእለ ያስተእኅዙ ቤተ ምስለ ቤት፤ ወለእለ ያስተቃርቡ ገራህተ ምስለ ገራህት፤ ወጥቅመ ምስለ ጥቅም ከመ ይሂዱ ዘኢኮነ ዚአሆሙ፤[፬]

፲፮. ወካዕበ ይቤ አእምሩ አንትሙ እለ ትነብሩ ዲበ ምድር ከመ ትስምዑ ዘንተ ነገረ ከመ በጽሐ ነገርክሙ ውስተ እዘኒሁ ለእግዚአ ብሔር ጸባኦት፡፡ በውስተ ካልዕኒ ይብል «ርጉመ ለይኩን ኵሉ ዘይ ሰርቅ ደወለ ቢጹ ወይበል ሕዝብ ለይኩን፤ ወበእንተዝ፤ ይብል

፫. ማቴ ፭ - ፳፰

፲፫.እኔ ግን ሴትን አይቶ የተመኛ ት ሁሉ ፈጽሞ አመነዘረባት ብዬ እነግራችኋለሁ፡፡

፲፬. ዳግመኛም እንደዚህ ይሠራ ዘንድ የሚወድ ሰው ከዘማውያን ጋራ ይፈረድበታል፡፡

፲፭. እነሆ በሬውን ወይም አህያ ውን ወይም እርሻውን በግፍ ይቀማ ዘንድ በልቡ የሚያስብና የሚመኝ እንዲህም እያደረገ የሚኖር ከዘማውያን ጋራ ይቈ ጠራል፤የራሳቸው ያልሆነውን ይቀሙ ዘንድ ቤትን ከቤት ጋራ ለሚያያይዙ ፣ እርሻንም ከእርሻ ጋር፣ ለሚያቀራርቡ ቅጥርንም ከቅጥር ጋር ለሚያቀራርቡ ወዮ ላቸው ተብሎ በነቢይ ተነግሮ አልና፡፡

፲፮.ዳግመኛም እንዲህ አለ፤ በምድር ላይ የምትኖሩ እናንተ ሆይ፤ ነገራ ችሁ ወደ ሠራዊት ጌታ ወደ እግ ዚአብሔር ጆሮዎች እንደ ደረሰ ይህን ነገር ትሰሙ ዘንድ ዕወቁ፤ በሌላም ክፍል ውስጥ የወንድሙን ድንበር የሚሰርቅ ርጉም ይሁን፤ ሕዝቡም ይሁን (አሜን) ይበል

ሙሴ «ኢትፍቱ ደወለ ካልእከ ወኢትንስት ሕገ ዘሠርዑ አበዊከ»[፭]

፲፯. ወእንበይነዝ ይብል ይከውን ፍርሀት፣ ወሞት፣ ወሀከክ፣ ወይረክቦሙ ሎነኔ እንተ እምነበ እግዚአብሔር ለእለ ይገብሩ ከመዝ::

፲፰ ወሰብእሰ እለ ያጸምዑ ቃለ እግዚአብሔር ፣ ወየዐቅቡ ሕጎ ብሩሀ በአማን ይረክቡ ሣህለ ወምሕረተ፣ እስመ ይቤ ዘትጸልእ ለርእስከ ኢትግበር ዲበ ቢጽከ[፮]፣ ወበከመ ኢትፈቅድ አንተ ይርአይ ባዕድ ብእሲተከ ወኢመኑሂ ከመ ያስሕታ በእከይ፣ ወከማሁ አንተኒ ኢትነጽር ብእሲተ ባዕድ በእኩይ ሕሊና፣ ወበከመ ኢትፈቅድ ይንሣእ ልብሰከ ካልእ ከማሁ አንተሂ ኢትንሣእ ልብሰ ባዕድ፣ ወበከመ ኢትፈቅድ ለርእስከ መርገመ ወፅዕለተ፣ ወዝብጠተ፣ ከማሁ አንተኒ ኢትግበር በካልእከ::

ሙሴም ስለዚህ ነገር እንዲህ ይላል «የወንድምህን ድንበር አትሻ አባቶችህም የሠሩትን ሕግ አታፍርስ»::

፲፯. ስለዚህም ነገር ፍርሀት ሞትና ክርክር ይሆናል፤ እንደዚህም የሚያደርጉትን ሰዎች ከእግዚአብሔር ዘንድ ቅጣት ያገኛቸዋል::

፲፰. የእግዚአብሔርን ቃል ሰምተው ብሩህ ሕጉን የሚጠብቁ ሰዎች ግን ይቅርታንና ምሕረትን ያገኛሉ ፤ ለራስህ የምትጠላውን በባልንጀራህ ላይ አታድርግ ብሏልና፤ አንተ ሌላው ሰው ሚስትህን ያይ ዘንድ ማንም በተንኰል ያስታት ዘንድ እንደማትወድ እንደዚሁ አንተም የሌላውን ሚስት በክፉ ሕሊና አታስብ፤ ሌላውም ልብስህን ይወስድብህ ዘንድ እንደማትወድ እንደዚሁ አንተም የሌላውን ልብስ አትውሰድ፤ ለራስህም መርገምን ስድብንና መመታትን እንደማትወድ እንደዚሁ አንተም በሌላው አታድርግ::

---

፭. ዘዳግ. ፲፱ +፲፪

፮ ማቴ. ፭ + ፲፪



፲፱. ወለእመቦ ዘረገመከ ወአንተሰ ባርክ እስመ ጽሑፍ ዘይብል ውስተ መጽሐፈ ኍልቍ «እለ ይባርኩከ ቡሩካነ ለይኩኑ፤ ወእለ ይረግሙከ ርጉማነ ለይኩኑ»[፯] ::

፳. ወዓዲ ጽሑፍ ውስተ ወንጌል «ደኀርምሙ ለእለ ይረግሙክሙ ወጸልዩ ዲበ እለ ይትዔገሉክሙ አላ ተዐገሥዎሙ፤ ወግበሩ ሠናየ ለእለ ይጸልኡክሙ ወኢትፍድዩ እኩየ ለእለ ይትዔገሉክሙ አላ ተዐገሥዎሙ»[፰] ፤ እስመ ይብል መጽሐፍ ኢትትበቀል ጸላኤከ ሀየንተ ዘገብረ ለከ እኩየ::[፱]

፳፩. ወበእንተዝ ይረድአከ እግዚአብሔር ወያገብእ ሎነኔ ላዕለ ጸላኢከ እስመ ይብል በወንጌል «አፍቅሩ ጸላዕተክሙ ወጸልዩ በእንተ እለ ይሰድዱክሙ ከመ ትኩኑ ውሉዶ ለአቡክሙ ዘበሰማያት እስመ ውእቱ ያሠርቅ ፀሐየ ላዕለ እኩያን ወኄራን ወያዘንም ዝናመ ላዕለ ጻድቃን ወዐማፅያን»[፲] ::

፳፪.አ ፍቁራኒነ ንለቡ እሉንተ ትእዛዛተ ከመ ንኩን ውሉደ ብርሃን ወተዐገሡ በበይናቲክሙ አ ውሉደ እግዚአብሔር ::

፲፱. የረገመህም ቢኖር አንተ መርቅ፤ በኦሪት ዘኍልቍ «የሚመርቁህ የተመረቁ ይሁኑ፤ የሚረግሙህም የተረገሙ ይሁኑ» የሚል ጽሑፍ አለና::

፳. ዳግመኛም በወንጌል እንዲህ ተጽፎአል«የሚረግሙአችሁን መርቋቸው፤ ለሚቀሟችሁም ጸልዩ ፤ ለሚጠሉአችሁም በጎ ሥራን አድርጉ፤ ለሚቀሙአችሁም ክፉ አትመልሱ» «ነገር ግን ታገሡአቸው፤ መጽሐፍ እንዲህ ይላልና «ክፉ ስለ አደረገብህ ጠላትህን አትበቀል» ይላልና::

፳፩. ስለዚህም ነገር እግዚአብሔር ይረዳሃል፤ፍርድንም በጠላትህ ላይ ይመልሳል፤ በወንጌል እንዲህ ብሏልና «የሰማያዊ አባታችሁ ልጆች ትሆኑ ዘንድ ጠላቶቻችሁን ውደዱ ፤ ስለሚያሳድዷችሁም ጸልዩ፤ እርሱ ለክፉዎችም፣ ለበጎዎችም ፀሐይን ያወጣልና፣ ለጻድቃንም ለኃጥአንም ዝናምን ያዘንማል ብሏልና::

፳፪. ወዳጆቻችን ሆይ፤ የብርሃን ልጆች እንሆን ዘንድ እነዚህን ትእዛዛት እናስተውል፤የእግዚአብሔር ልጆች ሆይ ፤ እርስ በርሳችሁ ትዕግሥትን ያዙ::

---

፯. ዘኍል. ፳፬ ፣፫

፰. ሉቃ ፮ ፣ ፳፰-፴፱

፱. ምሳ. ፳ ፡ ፳፪

፲. ማ[illegible]

፳፫. ወብእሲኒ ይትዐገሣ ለብእሲቱ፤ ወኢይኩን ዕቡየ ወመደልወ አላ ይኩን መሓሬ ወራትዐ ወያሠንያ፤ ለባሕቲታ በፍቅር ወበትሕትና ኢየአድም ወኢይፍቱ ካልእተ ብእሲተ ከመ ኢታስሕቶ::

፳፬. ወእመሰ ዘመውከ ወገበርከ ከመዝ መዊተ ትመውት፤ ወይመጽእ ላዕሌከ መቅሠፍት እምኀበ እግዚአብሔር፤ ወትትኴነን መሪረ ኵነኔ፤ ወባሕቱ እመ ኀለይከ በልብከ ወዘመውከ ምስሌሃ ይከውነከ ኀጢአተ::

፳፭. ወእመሂ ተደለውከ ወተሠነይከ ከመ ታፍቅርከ ብእሲተ ካልእከ ጌገይከ ወኮንከ ላቲ ዕቅፍተ ወአዘመውካ፤ ወበእንተዝ ይመጽእ ላዕሌከ ኵነኔ፤ እስመ ይቤ እግዚአብሔር ኢትፍቱ ወኢትዘሙ፤ እስመ አስሐትካ በስነ ውርዙትከ ወላህየ ገጽከ ከመ ታፍቅርከ፤ ወበእንተ ዝ ተሳተፍከ ምስሌሃ ኀቡረ ውስተ ግብረ ኀጢአት ወመርገም::

፳፫. ወንድ ሚስቱን ይታገሣት፤ ትዕቢተኛና ግብዝም አይሁን፤ ነገር ግን የሚራራና ቅን ይሁን፤ ለብቻዋም በፍቅርና በትሕትና ደስ ያሰኛት፤ እንዳታስተውም ሌላዪቱን ሴት አይውደድ፤ አይመኛትም::

፳፬. ብትሰስን እንደዚህም ብታደርግ ግን ሞትን ትሞታለህ፤ ከእግዚአብሔር ዘንድም መቅሠፍት ባንተ ላይ ይመጣል፤ መራራ ፍርድም ይፈረድብሃል ፤ ነገር ግን በልብህ አስበህ ከእርሷ ጋራ ብትሰስን ኀጢአት ይሆንብሃል::

፳፭. የባልንጀራህም ሚስት ትወድህ ዘንድ ብትዘጋጅና ብታጌጥ በደልህ ፤ ለእርሷም መሰናክል ሆንህ ፤ አሰሰንካትም፤ ስለዚህም ነገር ባንተ ላይ ፍዳ ይመጣል፤ እግዚአብሔር አትሰስን ፤ አትመኝም ብሏልና፤ ትወድህ ዘንድ በጐልማሳነትህ መልክና በፊትህ ደምግባት አስተሃታልና፤ስለዚህም በኃጢአትና በርግማን ሥራ ከርሷ ጋራ ተባበርክ ::



፳፮. ወበእንተዝ ይደልወከ ከመ ትስአሎ ለእግዚአብሔር አምላክከ ከመ ኢይርከብከ ዝንቱ ኵሉ ኀጢአት፤ ወባሕቱ አንተሰ መፍትው በንጽሕ ታሥምሮ ለእግዚአብሔር ከመ ትርከብ ዕረፍተ ወሕይወተ ዘለዓለም፡ በኀበ እግዚአብሔር፤ እስመ ይቤ ኢታንኀ ሥዕርተ ርእስከ አላ ዳዕሙ ቅርጽ ወአንጽሕ ርእሰከ ከመ ትትቀነይ ለእግዚአብሔር ወኢትትፈለጥ እምኔሁ::

፳፯. ወአንተሰ ኢትትቀባዕ ቅብዓ መዐዛ ወኢትልበስ አልባሰ ሠርጕ ለአስሕቶ አንስት ፤ ወኢትትመካሕ ወኢትኩን ማዕቀፈ አላ ኅሥሥ ንጽሐ ወገቢረ ሠናይ::

፳፰. ወአንተሰ ኦ ብእሴ እግዚአብሔር ኢታንኅ ሥዕርተ ርእስከ ኢትፍትል ወኢትጽፍሮ እስመ ዝንቱ ኵሉ ትእምርተ ርኵስ ወዝሙት ውእቱ ፤ እስመ ጽሑፍ ውስተ ዳግም ሕግ ወኢትልበስ ልብሰ ዘተአንመ በፀምር ወበአጌ፤ ወኢትግበር ለከ ዘፈረ ፍቱለ በልብስከ[፲፩]::

፳፮. ስለዚህም ይህ ሁሉ ኃጢአት እንዳያገኝህ እግዚአብሔርን ትለምነው ዘንድ ይገባሃል፤ ነገር ግን አንተ በእግዚአብሔር ዘንድ ለዘለዓለም ሕይወትንና ዕረፍትን እንድታገኝ በንጽሕና እግዚአብሔርን ደስ ታሰኘው ዘንድ ይገባል ፤ ለእግዚአብሔር ትገዛ ዘንድ ከርሱም እንዳትለይ የራስህን ጠጉር አታሳድግ፤ ጠጉርህን ቍረጥ፤ ራስህንም ንጹሕ አድርግ ብሏልና::

፳፯. አንተ ግን ሽቱ ያለበትን ዘይት አትቀባ ፤ ሴቶችንም ለማሳት የጌጥ ልብስ አትልበስ ፤ አትመካ ፤ መሰናክልም አትሁን፤ ነገር ግን ንጽሕናንና በጎ ሥራ መሥራትን ፈልግ ::

፳፰. አንተ የእግዚአብሔር ሰው ሆይ ፤ የራስህን ጠጉር አታሳድግ፤ ሥሉሶ አትሠራ፤ ሹርባ አትሠራ፤ ይህ ሁሉ የርኵሰትና የዝሙት ኃጢአት ምልክት ነውና፤ በኦሪት ዘዳግም ከበግ ጠጉር ብዝት፣ ከተልባ እግር በሐር ጥጥ የተሠራ ልብስን አትልበስ የሚል፤ ጽሑፍ አለና ለልብስህም የተፈተለ ዘርፍን አታደርግለት::

፳፱.ወባሕቱ ኢመፍትው ለነ ንላጺ ጽሕመነ፤ ወኢንወልጥ ፍጥረተ ብእሲ ውስተ ካልዕ ግዕዝ፤ ወእመሰ ትገብር ከመዝ ኮንከ ውጹአ እምሕግ ፤ ወርኁቀ እምእግዚአብሔር ዘፈጠረከ በአርአያሁ ወበአምሳሊሁ።

፳፱. ነገር ግን ጽሕማችንን እንላጭ ዘንድ ለኛ አይገባንም፤ የሰውንም ተፈጥሮ ወደ ሌላ ባሕርይ አንለውጥ፤ እንዲህ ካደረግህ ግን ከሕግ የወጣህ ሆንህ ፤ በአርአያውና በአምሳሉ ከፈጠረህ እግዚአብሔርም የተለየህ ሆንህ።

፴. ወእመሰ ትፈቅድ ታሥምሮ ለእግዚአብሔር ኢትግበር እኩየ ወአርኅቅ እምኔከ ኵሎ ዘይጸልእ አምላክከ፤ ወኢትኩን ሰካሬ፤ ወኢታንሶሱ ውስተ መራኅብት ምስለ ዘማውያን ዘእንበለ ጥበብ ወአእምሮ፤ አላ አንተሰ ተቀነይ ወሕየው በግብረ እደዊከ ወኀሥሥ ትግበር ኵሎ ዘያሠምሮ ለእግዚአብሔር ወተዘከር ቃሎ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወትሉ ኪያሁ ኵሎ ጊዜ ።

፴. እግዚአብሔርን ደስ ታሰኘው ዘንድ ከወደድህስ ክፉ ሥራን አትሥራ፤ ፈጣሪህም የሚጠላውን ሁሉ ከአንተ አርቅ፤ ሰካራም አትሁን፤ ከዘማውያንም ጋራ በአደባባይ አትዙር፤ አእምሮ ጠባይዓዊን አእምሮ መንፈሳዊን ያዝ እንጂ ፤ አንተ ግን በእጆችህ ሥራ ጥረህ ግረህ ተመገብ እንጂ፤ እግዚአብሔርንም ደስ የሚያሰኘውን ሥራ ሁሉ ትሠራ ዘንድ ውደድ፤ ሁልጊዜም እሱን ትከተል ዘንድ የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስን ቃሉን አስብ።

፴፩. እስመ ይብል ዳዊት «ወዘሕጎ ያነብብ መዓልተ ወሌሊተ[፲፪]፤ ወእመሂ በፍኖት፤አው በውስተ ቤት፤ ወእመሂ እንዘ ትነውም አፍቅሮ ለእግዚአብሔር አምላክከ በኵሉ ልብከ ወበኵሉ ሐሊናከ ወበኵሉ ኀይልከ ከመ ትርከብ በኀቤሁ ሣህለ ወምሕረተ።[፲፫]

፴፩. ዳዊት በመዓልትም በሌሊትም ሕጉን የሚያነብ ብፁዕ ነው ብሏልና፤ በጐዳናም ቢሆን ፤ በቤትም ቢሆን፤ ስትተኛም ቢሆን፤ ከእርሱ ይቅርታንና ቸርነትን ታገኝ ዘንድ ፈጣሪህ እግዚአብሔርን በፍጹም ሕሊናህ፤ በፍጹም ልቡናህ፤ በፍጹም አእምሮህ ውደደው።

፲፪. መዝ. ፩ ፡ ፪

፲፫. ዘዳግ. ፮ ÷ ፭ - ፯



## አንቀጽ ፪

በእንተ ከመ መፍትው ለአብዕልት ይኅሥሡ አእምሮ ረባሕ እመጻሕፍት በኀይለ መንፈስ ቅዱስ ኵሎ ጊዜ ።

## ሁለተኛ አንቀጽ

በመንፈስ ቅዱስ ኀይል ከመጻሕፍት የተገኘውን ጥቅም ማወቅን ሁለ ጊዜ ይመረምሩ ዘንድ ለባለጸጎች እንደሚገባ ይናገራል።

፩. ወእመሰ ባዕል አንተ ወኢትፈቅድ ኪነ ወቅኔ እድ በዘትሴሰይ ወተሐዩ ቦቱ ኢትትሀከይ ወኢትንበር ጽሩዐ፤አላ ሑር ኀበ መሃይምናን ወንበር ምስለ እለ የኀብሩ ምስሌከ ሃይማኖተ፤ወተናገር ነገረ ሕይወት፤ ወአንብብ ዘውስተ መጽሐፈ ነገሥት፤ወነቢያት፤ ወዘምር መዝሙረ ስብሐት፤ ወአጽምዕ ቃለ ወንጌል ዘውእቱ ተፍጻሜተ ኵሉ ሕግ።

፩. አንተ ባለጸጋ ብትሆን እንድትመገብና በሕይወት እንድትኖር ጥበብንና ተግባረ እድን ባትሻም ሰነፍ አትሁን፤ሥራ ፈት ሆነህም አትኑር፤ነገር ግን ወደ ምእመናን ሄደህ በሃይማኖት ከአንተ ጋር ከሚተባበሩ ጋር አብረህ ኑር፤ የሕይወትንም ነገር ተናገር፤ በነገሥትና በነቢያት መጽሐፍ ውስጥ ያለውንም ተመልከት፤ የምስጋና መዝሙርን ዘምር፤ የሕግ ሁሉ ፍጻሜ የሚሆን የወንጌልንም ቃል ስማ ።

፪. ወረኅቅ እምኵሉ ቅኔ ዘአማልክተ አሕዛብ፤ ወኢያጽሕቀ ኵሉ ነገረ ከንቱ ዘኢይበቍዕ፤ ወኢትኅሥሥ ካልአ ሕገ ወሐሳውያነ ነቢያት እለ ይዌልጡ ወያማስኑ ሃይማኖተ፤ ምንተ እንከ ስእንከ እምውስተ ሕገ እግዚአብሔር ከመ ትሕሥሥ ትምህርተ አሕዛብ ።

፪. ከአሕዛብ አማልክት መገዛት ሁሉ ራቅ፤ ለማይረባ ለማይጠቅም ለከንቱ ነገር ሁሉ አትጨነቅ፤ ከወንጌል ልዩ የሚሆን ሕግንና ሃይማኖትን ለውጠው የሚያጠፉ ሐሰተኞች መምህራንን አትሻ፤የአሕዛብን ትምህርት ትሻ ዘንድ ከእግዚአብሔር ሕግ ከኦሪት፤ ከወንጌል ምን አጣህ?

፫. ወእመሰ ትፈቅድ ታእምር አንብቦ ኀይለ ትርጓሜ መጻሕፍት ኅሥሥ መጽሐፈ ነገሥት፣ ወእመሂ ጽሕቀ ትጠይቅ ኀበ ጠቢባን ወትምህርቶሙ ለነቢያት ብከ ኢዮብ ወሰሎሞን፣ እሉ እሙንቱ ምሉአነ ጥበብ፤ ወትረክብ በኀቤሆሙ አእምሮ እለ ያፈደፍዱ ለብዎ እምኵሉ መምህራን፣እስመ ነገሮሙ ቃለ እግዚአብሔር አምላክ ዘውእቱ ባሕቲቱ ጠቢበ ጠቢባን ወእመሰ ትፈቅድ ማኅሌተ ብከ መዝሙረ ዳዊት፤ ወእመሂ ተኀሥሥ ትለቡ ፍጥረተ ዓለም ወልደተ አበው ቀደምት ብከ ኦሪት፣ ወእመኒ ትፈቅድ ታእምር ጥበበ ወትምህርተ ብከ መጽሐ ፈ ሕግ ዘምሉእ ውስቴቱ ስብሐተ እግዚአብሔር አምላክ።

፬. ረኀቅ እንከ እምግብር እኩይ ወትምህርተ ሰይጣን ወነገረ ከንቱ ዘኢሀለዉ ውስተ ሕግ፣ አላ አንብብ ውስተ ዳግም ሕግ ከመ ትለቡ ወትጠይቅ ስብሐቶ ለእግዚአብሔር ዘአድኀነከ እምብዙኀ መሣግሪሁ ለሰይጣን፣ እስመ ኢመጽአ መድኅን ከመ ይንሥቶሙ ለኦሪት ወለነቢያት አላ ከመ

፫. የመጻሕፍትን ትርጓሜ መመልከትንስ ታውቅ ዘንድ ብትወድ የነገሥትን መጽሐፍ ተመልከት፤ የመተርጕማንን ዕውቀት፣ ትምህርታቸውንም ትረዳ ዘንድ ብትተጋ ኢዮብ፤ ሰሎሞን አሉልህ፤ እሊህም ጥበብን የተመሉ ናቸው፤ ከመምህራን ሁሉ ዕውቀትን ከሚያበዙ ከእነርሱ ዕውቀትን ታገኛለህ፤ ነገራቸው ብቻውን የአዋቂዎች አዋቂ የሚሆን የፈጣሪ የእግዚአብሔር ቃል ነውና፤ ማኅሌትንስ ከወደድህ የዳዊት መዝሙር አለልህ፣ሥነ ፍጥረትን የቀደሙ አበውንም ልደት ብትሻ ኦሪት አለልህ፣ ትምህርትና ጥበብን ልታውቅ ብትወድ በውስጡ የፈጣሪ የእግዚአብሔር ጌትነት የተመላበት የሕግ መጽሐፍ አለልህ።

፬. እንግዲህ በሕግ ከሌሉ ከክፉ ሥራ ከሰይጣን ትምህርትና ከከንቱ ነገር ራቅ፣ ነገር ግን ከብዙ የሰይጣን ወጥመድ ያዳነህን የእግዚአብሔርን ጌትነት ታስተውልና ትረዳ ዘንድ ዳግም ሕግን አንብብ፤ ኦሪትን ነቢያትን· ያሳልፋቸው ዘንድ



ይፈጽሞሙ[፭] ወይፍታሕ ማእሠረ ዘውስተ ዳግም ሕግ ወያግብኦሙ ውስተ ትምህርት መንፈሳዊት፤ ወበእንተዝ ይጼውዕነ እንዘ ይብል ንዑ ኀቤየ ኵልክሙ ጽዑራን ወክቡዳነ ፆር ወአነ አዐርፈክሙ። [፮]

፭. ወአንተሰ እምከመ አንበብከ ኦሪተ፣ ወነቢያተ፣ ወነገሥተ፤ ወወንጌለ ትሌቡ ሚመጠን ዕደው ጻድቃን እለ ነግሡ ወአሥመርዎ ለእግዚአብሔር በሕይወቶሙ፤ ወበእንተዝ ረከቡ ሕይወተ ዘለዓለም፣ ወዓዲ ተአምር ስፍነ ነገሥተ ርኩሳነ እለ ዐለዉ በኢሉብዎቶሙ፤ ወእሙንቱሰ ማሰኑ ወጠፍኡ በመቅሠፍተ መዓቱ፤ ተኰነኑ ወኀጕሉ ሕይወተ ዘለዓለም፣ ወአመጠየቀ ዘንተ ትጸንዕ በርትዕት ሃይማኖት፤ ወትረክብ ጸጋ ወሞገሰ በኀበ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ እስመ ኮንከ ሎቱ አባለ።

፮. ወአንተሰ ሶበ ትፈቅድ ትትሐፀብ ኢትባእ ውስተ ቤተ ብለኔ ኀበ ይትሐፀባ አንስት፤ ከመ ኢይርአያ ሥነ ውርዙትከ ወላህየ ሥጋከ፣ ወኢይትዐቀፋ ብከ ወለሊከኒ ኢተአብስ፤ ወኢትድኀፅ ቦቶን ።

፭. ማቴ ፭ : ፲፯

አልመጣምና በዳግም ሕግ የነበረውን እስራት ይፈታ ዘንድ ወደ መንፈሳዊ ትምህርት ወደ ወንጌልም ይመልሳቸውና ይፈጽማቸው ዘንድ ነው እንጂ፤ ስለዚህም እናንተ ደካሞች ሸክማችሁ የከበደ ሁላችሁ ወደኔ ኑ፤ እኔም አሳርፋችኋለሁ እያለ ይጠራናልና።

፭. አንተስ ኦሪትን፣ ነቢያትን፤ ነገሥትን፤ ወንጌልንም የተመለከትህ እንደሆነ በሕይወተ ሥጋቸው ነግሠው እግዚአብሔርን ደስ ያሰኙት ጻድቃን ሰዎች ምን ያህል እንደሆኑ ታውቃለህ፤ ስለዚህም የዘለዓለም ሕይወትን አገኙ፣ ዳግመኛም ባለ ማወቃቸው የካዱ ርኩሳን ነገሥታት ስንት እንደ ሆኑ ታውቃለህ፤ እነርሱም በቍጣው መቅሠፍት ፍርድ ፈጽመው ጠፉ፣ የዘለዓለም ሕይወትንም አጡ ፣ ይህንንም ብትረዳ በቀናች ሃይማኖት ትጸናለህ፤ ከጌታችን ከኢየሱስ ክርስቶስ ዘንድም ባለሟልነትን ታገኛለህ ፤ ለእርሱ አካል ሁነሃልና።

፮. አንተ ግን ትታጠብ ዘንድ በወደድህ ጊዜ የሕፃንነትህን ደም ግባትና የሰውነትህን ማማር እንዳያዩ በአንተም እንዳይሰናከሉ፤ አንተም እንዳትበድል፣ በእነርሱም እንዳትሰነካከል፣ ሴቶች ወደሚታጠቡበት መታጠቢያ ቤት አትግባ።

፯. ንስማዕ ወንለቡ ቃለ ቅዱስ ዘይቤ መጽሐፈ ምሳሌ «ወልድየ ዕቀብ ነገረ ዚአየ፤ ወትእዛዘ ዚአየ ኅባዕ ኀቤከ»።

፰. ወበላ ለጥበብ እኅተ ዚኣየ አንተ፤ ወለአእምሮ ሀገሪተከ ረስያ።

፱. ከመ ትዕቀብከ እምብእሲት ነኪርት ወእኪት አመ ነገረ ዘርቅ አምጽአት ለከ ።

፲. እስመ እመስኮተ ቤታ ውስተ መራሕብት ትሔውጽ።

፲፩. ዘርእየት እምአብዳን ውሉድ ወሬዛ ነዳየ አእምሮ።

፲፪. ዘየሐውር በፍናወ ማእዘንተ ቤታ ወይትናገር።

፲፫. በጽልመት ሠርከ ሶበ ይከውን ጽማዌ ወጽልመተ ሌሊት።

፲፬. ወሶቤሃ ትዳደቆ ብእሲት እንተ ባቲ ትርሲተ ዝሙት፣ እንተ ትሬሲ ይሥርር ልበ ወራዙት።

፲፭. ሥርርትይእቲ ፤ ወምርዕት፤ ወበቤታኒ ኢየዐርፉ እገሪሃ ።

፲፮. ወምዕረ ኅዳጠ ታንሑት አፍኣ፤ ወምዕረ ኅዳጠ ውስተ መራሕብት፤ ወውስተ ኵሉ ማእዘንት ትጸንሕ።

፯. መጽሐፈ ምሳሌ የሚለውን ቅዱስ ቃል ሰምተን እናስተውል፤ «ልጄ ሆይ!ቃሌን ጠብቅ፤ ትእዛዜንም በአንተ ሸሽግ።

፰.ጥበብን አንቺ እኅቴ ነሽ በላት፤ ማስተዋልንም ወዳጅ አድርጋት፤

፱. ከባዕድና ከክፉ ሴት ዋዛ፣ ነገርንም ከምታመጣብህ ትጠብቅህ ዘንድ።

፲. በቤቷ መስኮት ሆና ወደ ዐደባባይ ትመለከታለችና።

፲፩. ከአላዋቂዎች ወጣቶች መካከል ከዕውቀት ድሃ የሆነውን ጐልማሳ ብታይ።

፲፪. በቤትዋም አቅራቢያ ባለው መንገድ ሲሄድ ሲናገርም።

፲፫. ማታ ሲመሽ ውድቅትም ሲሆን በሌሊት በጽኑ ጨለማ።

፲፬. የምንዝር ጌጥ ያላት የጐልማሶችን ልብ እንዲሰቀል የምታደርግ ሴት ያን ጊዜ ትገናኘዋለች።

፲፭. እርስዋ የምትበርር፣ መዳራትንም የምትወድ ናት፤ በቤትዋም እግሮቿ አያርፉም ።

፲፮. አንድ ጊዜ በጐዳና፣ በሌላ ጊዜም በዐደባባይ፣ በማእዘኑም ሁሉ ታደባለች።



፲፯. አኀዘቶ ወሰዐመቶ ወዘእን በለ ኀፍረት ትቤሎ በገጽ።

፲፰. መሥዋዕተ ሰላምየ ውእቱ፤ ዮም ብፅዐትየ እሁብ።

፲፱. በእንተ ዝንቱ መጻእኩ እትቀበልከ፤ ወእንዝ አፈቅር ገጸ ዚአከ ረከብኩከ ።

፳. በቀጠንት ገለድኩ ምስካብየ፤ ወዘርቤታተ ነጸፍኩ ዘእምግብፅ።

፳፩. ነስነስኩ ምስካብየ መጽርየ፤ ወቤትየኒ በቀናንሞስ ።

፳፪. ነዓ ናስተሐውዝ በተሳዕሞ እስከ ነግህ ፤ ወናንገርግር በተፋቅሮ።

፳፫ እስመ ኢሀሎ ምትየ ውስተ ቤቱ፤ ወሖረ ፍኖተ ርኁቀ፤

፳፬. ነሢኦ ውስተ እዴሁ ዕቊረ ወርቅ፤ በመዋዕል ብዙኅ እመ ገብአ ውስተ ቤቱ።

፳፭. ወአስሐተቶ በብዙኅ ነገር፤ ወበመሥገርተ ከናፍር ሰሐበቶ።

፳፮. ወተለዋ ደኒና ከመ ላሕም ዘየሐውር ለተጠብሖ፤ ወከመ ከልብ ለተአሥሮ[*] ።

፳፯. ወዓዲ ይቤ «ኢትነጽር ብእሲተ እኪተ»።

፲፯. ያዘችውም፤ ሳመችውም፤ ፊትዋም ያለ ኀፍረት ሆና እንዲህ አለችው ።

፲፰. የፍቅሬ መሥዋዕት ነው፤ ዛሬ ስእለቴን እሰጣለሁ።

፲፱. ስለዚህ እንድገናኝህ መጣሁ፤ ፊትህንም ስሻ አገኘሁህ።

፳. በአልጋዬ ላይ ማለፊያ ሰርፍ ዘርግቼበታለሁ፤የግብፅንም ሽመል መሌ ምንጣፍ ዘርግቼበታለሁ።

፳፩. በመኝታዬ ዐልሙን፣ በቤቴም ቀረፋ ረጭቼበታለሁ።

፳፪.ና፤ እስኪነጋ ድረስ በመልካም መሳሳም ደስ ይበለን፤ በፍቅርም እንርካ ።

፳፫. ባለቤቴ በቤቱ የለምና፤ ወደ ሩቅ መንገድም ሄዶአልና ፤

፳፬. በእጁም የወርቅ ከረጢት ይዞ አል፤ ወደ ቤቱ ቢመለስም ከብዙ ጊዜ በኋላ ነው።

፳፭. በብዙ ጨዋታዋ ታስተዋለች፤ በከንፈርዋ ወጥመድም ትጎትተዋለች።

፳፮. እርሱም ለመታረድ እንደ ሚነዳ በሬ፣ ለመታሰርም እንደ ሚሔድ ውሻ አንገቱን ደፍቶ ይከተላታል።

፳፯. ዳግመኛም እንዲህ ይላል፣ «ወደ አመንዝራ ሴት አትመልከት»።

፳፰. እስመ መዓር ይውኅዝ እም ከናፍረ ብእሲት ዘማ፤ እንተ ለጊ ዜሁ ያመዐርዕሮ ለጕርዔከ።

፳፱. ወእምድኅሬሁሰ ዘይመርር እም ሐሞት ትረክብ፤ ወስሑል ፈድ ፋደ እመጥባሕት ዘክልኤ አፉሁ።

፴. ወካዕበ ይቤ ረሲ ርኁቀ ፍና ተከ እምኔሃ ፤ ወኢትቅረብ ኀበ ኆኅተ ቤታ።

፴፩. ከመ ኢትወስክ ለባዕድ ሕይወተከ፣ ወንብረተከ ለእለ ዘእ ንበለ ምሕረት።

፴፪. ከመ ኢይጽገቡ ነኪራን ኀይ ለከ፤ ወፃማ ዚአከ ቤተ ባዕድ ኢይባእ።

፴፫. ወትኔስሕ ድኅረ አመ ደክመ ሥጋ ነፍስትከ ወትብል።

፴፬. እፎ ጸላእኩ ትምህርተ፣ ወእ ምተግሣጽ ተግኅሠ ልብየ።

፴፭. ወኢሰማዕኩ ቃለ ዘይሜህ ሩኒ ወይጌሥጹኒ ወኢያጽማዕኩ በእዘንየ።

፴፮. ዘእንበለ ንስቲት ኮንኩ ውስተ ኵሉ እኩይ ማእከለ ማኅበር ወእ ንግልጋ[፬] ።

፳፰. ከአመንዝራ ሴት ከንፈር ማር ይንጠባጠባልና ፣ ለጊዜው ጉረሮህን ያጣፍጠዋል።

፳፱. በኋላ ግን ከሐሞት የመረረ ሁኖ ታገኛለህ፤ ሁለት አፍ ካለው ሰይፍ ይልቅም የተሳለ ነው።

፴. ዳግመኛም እንዲህ ይላል፣ መንገድህን ከእርስዋ አርቅ ፤ ወደ ቤትዋም ደጅ አትቅረብ፤

፴፩. ሕይወትህን ለሌላ እንዳት ሰጥ፣ ንብረትህንም ምሕረት ለሌ ላቸው ።

፴፪. ባዕዳን ሀብትህን እንዳይጠ ግቡ ፣ የድካምህም ፍሬ በባዕድ ሰው ቤት እንዳይገባ።

፴፫. ሰውነትህ በደከመ ጊዜ ኋላ ትጸጸታለህ፤ እንዲህም ትላለህ።

፴፬. እንዴት ትምህርትን ጠላሁ? ልቤም ከተግሣጽ እንዴት ራቀ?

፴፭. የአስተማሪዎቼንም ቃል አል ሰማሁም ፤ በጆሮቼም አላዳመጥ ሁም።

፴፮. በማኅበርና በጉባኤ መካከል ወደ ክፉ ሁሉ ለመድረስ ጥቂት ቀረኝ ፤

፬. ምሳ. ፭ + ፲፬



፴፯. ወይእዜኒ እብለክሙ ኅረዩ ኵሎ ሠናያተ እለ ጽሑፋት ውስተ ቅዱሳት መጻሕፍት ከመ ኢናስትት እሎንተ ስምዓተ፤ ወኢ ንትመየጥ ውስተ ብዙኅ ነገር።

፴፰. አላ ንጽናዕ በሃይማኖት ወበ ገቢረ ሠናይ፤ ወንርኃቅ እምኵሉ ምግባር እኩይ፤ ወንኩን ንጹሓነ እምኵሉ እኩይ ወርኵስ በቅድመ እግዚአብሔር ከመ ንርከብ ሕይ ወተ ዘለዓለም።

## አንቀጽ ፫

በእንተ ከመ መፍትው አንስት ይትአዘዛ ለአምታቲሆን፣ ወይሑራ በጥበብ።

፩. ርቱዕ ብእሲት ትትአዘዝ ወት ተሐት ለምታ፣ እስመ ርእሳ ለብእ ሲት ምታ፤ ወርእሱ ለብእሲ ዘየ ሐውር በፍኖት ርቱዕ ክርስቶስ፣ ወርእሱኒ ለክርስቶስ እግዚአብ ሔር አብ፤[፩] አኃዜ ኵሉ ዘሀሎ ወይሄሉ ፈጣሬ ኵሉ ምስለ ወልዱ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ዘሎቱ ዕበይ፣ ወክብር፣ ወልዕልና፣ ወስብሐት።

፪. ወአንትንሂ አንስት ተአዘዛ ለአ ምታቲክን፤ ወተቀነያ በክብር ወበፈ ሪሀ እግዚአብሔር ወአስተፍሥሓ አምታቲክን በሠናይ ቅኔ፤ ከመ ትርከባ ሞገሰ በኀቤሆሙ በከመ አቅደምነ ነጊረ።

[illegible]

፴፯. አሁንም እንዲህ እላችኋለሁ፣ እነዚህን ምስክሮች እንዳናቃልል ወደ ብዙ ነገርም እንዳንመለስ በቅ ዱሳት መጻሕፍት የተጻፉትን በጎ ነገ ሮችን ሁሉ ምረጡ።

፴፰. በሃይማኖትና በጎ በመሥራ ትም እንጽና፤ ከክፉ ሥራም ሁሉ እንራቅ፣ የዘለዓለም ሕይወትንም እናገኝ ዘንድ ከክፉ ሁሉና ከር ኵሰት በእግዚአብሔር ፊት ንጹ ሓን እንሁን።

## ሦስተኛ አንቀጽ

ሴቶች ለባሎቻቸው ይታዘዙ ዘንድ፣ በቀናም ጥበብ ጸንተው ይኖሩ ዘንድ እንዲገባ ይናገራል።

፩. ሴት ለባሏ በትሕትና ትታዘዝ ለሴት ራሷ ባሏ ነውና፣ በቀና መንገድ ለሚኖር ወንድም ራሱ ክርስቶስ ነው፣ ለክርስቶስም ራሱ ሁሉን ቻይ፤ የነበረና የሚኖር ገናናነትና ክብር ልዕልናና ምስጋና በሚገባው በልጁ በጌታችን በኢየ ሱስ ክርስቶስ ሁሉን የፈጠረ እግዚአብሔር አብ ነው ።

፪. እናንተም ሴቶች ለባሎቻችሁ ታዘዙ፤እግዚአብሔርንም በመፍራ ትና በማክበር ተገዙ፤ አስቀድመንም እንደተናገርን ከእነርሱ መወደድን እንድታገኙ በበጎ አገልግሎት ባሎ ቻችሁን ደስ አሰኙ።

፫. እስመ ከመዝ ይብል ተግሣጸ ሰሎሞን መኑ ይረክባ ለብእሲት ጽንዕት፣ ክብርት ይእቲ እምዕንቊ ክቡር ዘብዙኅ ሤጡ ::

፬. ለእንተ ከመዝ ብእሲት ይትአመን ባቲ ልበ ምታ ወእንተ ከመዝ እምሠናይ ምህርካ ኢታሐፅዖ::

፭. ትረድኦ ለምታ ሠናየ በሠናይ፣ ወአኮ እኩየ በእኩይ በኵሉ መዋዕለ ሕይወታ::

፮ እንዘ ትቤዝት ፀምረ ወአጌ፣ ገብረት ሠናየ በእደዊሃ::

፯. ኮነት ከመ ሐመር እንተ ትትጌበር እምርኁቅ፣ ወታስተጋብእ ላቲ ኵሎ ብዕለ::

፰. ወትትነሣእ በሌሊት ወትሁብ ሲሳየ ለሰብአ ቤታ ወግብሮን ለአዋልድ::

፱. ርእየት ወፍረ፤ ወተሣየጠት፤ ወእምፍሬ እደዊሃ ተከለት ጥሪተ::

፲. አጽኒዓ ወቀኒታ ሐቌሃ አውፅአት እዴሃ ለግብር ::

፲፩. ጥዕመት ከመ ሠናይ ውእቱ ተቀንዎ፤ ወኢይጠፍእ ዙሉ ሌሊተ ማኅቶታ::

፫ ተግሣጸ ሰሎሞን እንዲህ ይላልና፣ ልባም ሴትን ማን ያገኛታል? ዋጋው ብዙ ከሆነ ከከበረ ዕንቊ እጅግ የከበረች ናት ::

፬. እንደዚህ ባለችዋ ሴት የባልዋ ልብ ይታመንባታል፤ እንደዚህ ያለችውም ከመልካም ምርኮ አታሳንሰውም::

፭. ዕድሜዋን ሙሉ በክፉ ላይ ክፉ ያይደለ በበጎ ላይ በጎ እየሠራች ባሏን ትረዳዋለች::

፮. የበግ ጠጕርንና የተልባ እግርን እያባዘተች በእጆችዋ መልካም ትሠራለች::

፯. እርስዋ ከሩቅ እንደምትነግድ ሀብትንም ሁሉ እንደምትሰበስብ መርከብ ሆነች::

፰. በሌሊት ትነሣለች፤ ለቤተሰብዎቿ ምግባቸውን ትሰጣለች፤ ለሠራተኞችዋም ተግባራቸውን ትሰጣለች::

፱. እርሻን ተመልክታ ትገዛለች፤ ከእጆችዋም ፍሬ ጥሪትን ትተክላለች::

፲. ወገብዋንም አጽንታ ታጥቃ እጆቿን ለሥራ ታወጣለች::

፲፩. ሥራ መልካም እንደሆነ ትመለከታለች፤ መብራትዋም ሌሊቱን ሁሉ አይጠፋም::



፲፪. ወእደዊሃ ትሰፍሕ ዲበ ዘይበቍዕ፤ ወዕመታ ታጸንዕ ለፈቲል::

፲፫. ወእደዊሃ ትፌትሕ ላምስኪን፣ ወእራኃ ትሰፍሕ ለነዳይ::

፲፬. ወኢይቴክዝ ምታ በእንተ ቤቱ እመቦ ኀበ ጕንደየ ወኵሎሙ እሊኣሃ እሩዛን እሙንቱ በበክልኤ::

፲፭. ክዑበ ከለሜዳ ገብረት ለምታ ዘቢሶስ፤ ወሜላተ ገብረት ላቲ አልባሰ::

፲፮. ወዘያስተርኢ ይከውን ምታ በውስተ አናቅጽ ሶበ ይነብር ውስተ ማኅበር ምስለ ሊቃናተ ምድር::

፲፯. ሰንዱናተ ገብረት፤ ወሤጠት፤ወንቊበታተ ለከነናውያን፤ ወአፉሃ ከሠተት ዘበሕግ፤ ወአቀመት ሥርዐተ ለልሳና::

፲፰. ኀይለ ወላህየ ለብሰት ወተፈሥሐት በመዋዕል ደኃርያት::

፲፱. ወጽፉቅ በዋኤ ቤታ ወኍበስተ ሀኬት ኢበልዐት::

፳. ሕግ ወምጽዋት ውስተ አፉሃ፤ አፉሃ ትፌትሕ በጥበብ ወበሥ[illegible]

፲፪. እጆችዋንም ወደሚጠቅም ሥራ ትዘረጋለች፤ ክንድዋንም ለመፍተል ታበረታለች (ታጸናለች)::

፲፫. እጆቿን ለችግረኛ ትፈታለች፤ መሐል እጅዋንም ለድሀ ትዘረጋለች::

፲፬. ባሏም በውጭ የዘገየ እንደሆን ስለ ቤቱ አይጨነቅም፤ ቤተሰቦቿ ሁሉ ዕጥፍ ድርብ የለበሱ ናቸው::

፲፭. ለባልዋ ዕጥፍ ሆኖ ከተፈተለ የተልባ እግር መጐናጸፍያ ትሠራለች፤ ለራስዋም ከነጭ ሐር ልብስን ትሠራለች::

፲፮. ባልዋ በሀገር ሽማግሌዎች መካከል በሸንጎ በሚቀመጥ ጊዜ በዐደባባይ የታወቀ(የሚታይ) ይሆናል::

፲፯. የበፍታ ቀሚስ እየሠራች ትሸጣለች፤ ለከነናውያንም ድግ ትሸጣለች፤ ሕጋዊ በሆነ ነገር አፍዋን ትከፍታለች፤ ለአንደበትዋም መጠንን ታደርጋለች::

፲፰. ብርታትንና ውበትን ትለብሳለች በኋላም ዘመን ላይ ደስ ይላታል::

፲፱. ወደ ቤቷ የሚገባ ብዙ ነው፣ የስንፍና እንጀራንም አትበላም::

፳. ሕግና ምጽዋት በአፍዋ አለ፤ አፍዋን በጥበብና ሕግ ባለው ሥርዐት ትከፍታለች::

፳፩. ወምጽዋታ አልሀቀ ውሉደ ወአብ ዐለ፣ ወምታ ወደሳ።

፳፪. ብዙኃት አዋልድ አጥረያ ብዕለ፤ ወብዙኃት ገብራ ኀይለ፤ ወአንቲሰ ትፈደፍዲ፤ ወተዐደውኪ ኵሎን።

፳፫. ሕስው አሥምሮ፣ ወምኑን ላህይ፤ እስመ ብእሲት ጠባብ ትት ባረክ፣ ወፈራሂተ እግዚአብሔር ይእቲ ትሴባሕ።

፳፬. ሀብዋ እምፍሬ ከናፍሪሃ፣ ወይት አኰት በአናቅጽ ምታ[፪] ።

፳፭. አእምራ አንስት ከመ ብእሲት እንተ ታፈቅር ምታ ትረክብ ክብረ በኀበ እግዚአብሔር አምላክ።

፳፮. ዑቂ ወለብዊ ኦ ብእሲት እንተ ታፈቅሪ ወትፈቅዲ ትኩኒ መሃይምንተ ከመ ታሥምሪዮ ለእግ ዚአብሔር፤ ወኢትትመክሒ ወኢት ሠነዪ ለካልእ ብእሲ ፤ ወኢትልበሲ አልባሰ ሠርጕ፤ ወኢትደዪ አሣዕነ ውስተ እግርኪ በትዝኅርት፤ በከመ ይገብራ አንስት ዘማት ለአስሕቶ ፣ አላ ተዐቀቢ እም

፪. ተግሣጽ ፳፱ + ፴፩

፳፩. ምጽዋትዋ ልጆችን ያሳድጋል፤ ያበለጥጋልም፤ ባልዋም እንዲህ ሲል ያመሰግናታል።

፳፪. ብዙ ሴቶች ልጆች ሀብትን ሰበሰቡ፤ ብዙዎቹም ኀይልን አደረጉ፤ አንቺ ግን ትበልጫለሽ፤ ከሁሉም ትልቂያለሽ ።

፳፫. ውበት ሐሰት ነው፤ ደም ግባ ትም የተናቀ ነው፤ ብልህ ሴት ትባረካለችና ፣ እግዚአብሔርንም የምትፈራ እርስዋ ትመሰገናለች።

፳፬. ከከንፈርዋ ፍሬ ስጡአት፤ ባልዋም በዐደባባይ ይመሰገናል።

፳፭. ሴቶች ሆይ! ባልዋን የምትወድ ሴት በፈጣሪ እግዚአብሔር ዘንድ ክብርን እንደምታገኝ ዕወቁ።

፳፮. እግዚአብሔርን ደስ ለማሰ ኘት የታመንሽ ትሆኚ ዘንድ የምትወጂና የምትፈቅጂ ሴት ሆይ! ዕወቂ፤ አስተውዪ፤ አትመ ኪም፤ ለሌላ ወንድም አትዋቢ፤ የጌጥ ልብሶችንም አትልበሺ፤ ሴሰ ኞች ሴቶች ሰውን ለማሳት እንደ ሚያደርጉ በትዕቢት በእግርሽ ጫማ አታድርጊ ፤ ነገር ግን ሌሎች በአንቺ እንዳይሰናከሉ



ኵሉ ምግባር እኩይ ወዝሙት፤ ከመ ኢይትዐቀፉ ብኪ ካልኣን ዳዕሙ ተዐዘዚ ለምትኪ ወአሠንዪ ሎቱ።

፳፯. ወእመሰ ትፈቅዲ አንሶስዎ በውስተ ማኅበር ወመራኅብት ለአ ሥግሮ ነፍስ ብዙኀ ጊዜ፣ ይመጽእ ላዕሌኪ ኵነኔ እምኀበ እግዚአብ ሔር ፣ ወትከውኒ ዘአልባ ተስፋ።

፳፰. ከመ ሶበ ረሲዕ ይወድቅ ውስተ ዐቢይ ምንዳቤ ወያመጽእ ለርእሱ ነውረ ወኃሣረ ወኀዘነ ከማሁ እኪት ብእሲት ታመጽእ ለርእሳ ኃሣረ።

፳፱. ወከመ አንበሳ ዘይጸንሕ ወይመስጥ ከማሁ ታሠግሮሙ ለአብዳን፤ እስመ ጽሑፍ ዘይብል ከመ ቍንቍኔ ለልብስ ወከመ ነቀዝ ለዕፅ[፫] ወከማሁ ኀዘን ታማስኖ ለብ እሲ ልቦ ።

፴. ወዓዲ ይቤ ይኄይስ ነቢር ውስተ ገዳም እምትንበር ምስለ ብእሲት መግዐዚት ወነባቢት ወመ ዐትምት[፬]።

፴፩. ይእዜኒ ንብለክሙ ኦ ሕዝበ ክርስቲያን ኢትነጽሩ ፤ ወኢትትልዉ ዘማተ አንስተ።

፫. ተግሣፅ ፩ + ፳
፬. ምሳ ፳፩ + ፲፱

ከክፉ ሥራ ሁሉና ከዝሙት ተጠ በቂ፤ ለባልሽም ታዘዢ፣ ለእር ሱም መልካም አድርጊለት።

፳፯. ብዙ ጊዜ ሰውን ለማሳት በጉባኤና በዐደባባይ መመላለስን ብትወጂ ግን ከእግዚአብሔር ዘንድ በአንቺ ላይ ቅጣት ይመጣብ ሻል፣ ተስፋ የሌላት ትሆኛለሽ።

፳፰. ዝንጉ ሰው በታላቅ መከራ እንደሚወድቅ በራሱም ነውርንና ውርደትን፣ ኀዘንንም እንደሚ ያመጣ እንደዚሁ ክፉ ሴት ለራ ስዋ ውርደትን ታመጣለች።

፳፱. ሽምቆ እንደሚነጥቅ አንበሳ እንደዚሁ አላዋቆችን ታጠምዳቸዋ ለች፤ ብል ልብስን፤ነቀዝም ዕንጨ ትን እንዲያጠፋ፣ እንዲሁም ኀዘን የሰውን ልቡና ታጠፋዋለች ተብሎ ተጽፎአልና።

፴. ዳግመኛም ከተጨቃጫቂ ከቀባ ጣሪና ከቍጡ ሴት ጋራ ከመኖር በበረሃ መኖር ይሻላል ይላልና።

፴፩. አሁንም የክርስቲያን ወገኖች ሆይ፣ ሴሰኞች ሴቶችን አትመ ልከቱ አትከተሉ እንላችኋለን።

፴፪. ወባሕቱ ርቱዕ ለአንስት ምእመናት ይትገልበባ ርእሶን በንጽሕ ወኢኮ በአሠንዮ ላህየ ገጾን ወጥምዐታት፣ ወተኰህሎ ወተሠርግዎ ዘአልቦ ባቍዕ ውስተ መልክዕ ዘፈጠረ እግዚአብሔር፤ ወኢይግበራ ከመዝ አላ ሰበ የሐውራ በፍኖት ያድንና ርእሶን እንዘ ግልቡባት እማንቱ፤ ወዕቀባ ርእሰክን ኦ ምእመናት ወኢትትናገራ ጽልአ ወኢምስለ መኑሂ ወፈድፋደሰ ለአምታቲክን ::

፴፫. ኦ አንስት ኄራት፣ ወየዋሃት አምልካሁ ለእግዚአብሔር በፍሥሐ ወበሐሤት::

፴፬. ወአንትሙኒ ደቂቅነ ወአኃዊነ ወአዝማዲነ ወፍቁራኒነ ኅሥዋ ለክብርት ጥበብ እንተ ታሤኒ ግዕዘነ ወታበርህ አልባቢነ ፣ ወታቀርበነ ኀበ እግዚአብሔር ወታበውአነ ውስተ መንግሥተ ሰማያት ውስተ ሕይወት ዘለዓለም ወዕረፍት::

## አንቀጽ ፭

በእንተ ኤጲስ ቆጶስ፣ ወቀሲስ፣ ወዲያቆናት::

፴፪. ነገር ግን ላመኑ ሴቶች ራሳቸውን በንጽሕና ሊከናነቡ ይገባል፤ የፊታቸውን ውበት በማሳመርና ቀለም በመቀባት አይደለም፤ እግዚአብሔር በፈጠረው መልክ ውስጥ ጥቅም በሌለው ኵል መኳልና ማጌጥም አይደለም ፣ እንዲህ ያለውንም ሁሉ አይሥሩ፤ ነገር ግን እነርሱ ተከናንበው በጎዳና ራሳቸውን ዝቅ አድርገው ይሂዱ፤ ምእመናት ሆይ! ራሳችሁን ጠብቁ፤ ከማንም ጋር አትነጋገሩ ፤ ይልቁንም ከባሎቻችሁ ጋር ጥላቻን አትነጋገሩ::

፴፫. ደጋጎችና የዋሆች ሴቶች ሆይ! በደስታና በሐሴት እግዚአብሔርን አምልኩት::

፴፬. እናንተም ልጆቻችን፣ ወንድሞቻችን፣ ዘመዶቻችንና ወዳጆቻችን ጠባይን የምታሳምር፣ ልቡናችንን ብሩህ የምታደርግ፣ ወደ እግዚአብሔርም የምታቀርበንን ለዘለዓለም ሕይወትና ዕረፍት ወደ መንግሥተ ሰማያት የምታስገባን የከበረች ጥበብን ፈልጓት ::

## አራተኛ አንቀጽ

ስለ ኤጲስ ቆጶስ፤ ስለ ቄስና ስለ ዲያቆናት ይናገራል::



፩. ወበእንተ ኤጲስ ቆጶስ ሰማዕነ ከመዝ በኀበ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ከመ መፍትው ይኩን ኖላዌ አባግዕ ዘይሠየም ኤጲስ ቆጶሰ ለኵሉ አብያተ ክርስቲያናት ዘአልቦ ነውር፣ ንጹሕ ወኄር፣ ወዘኢይኄሊ ትካዘ ዘዝንቱ ዓለም፤ ወዘአጠንቀቀ ፶ ዓመተ፣ወዘፈጸመ ኀይለ ውርዙት፣ ዘኢኮነ መስተዋድየ ፣ ወዘኢይነብብ ሐሰተ ማዕከለ አኀው::

፪. እስመ ይብል ወንጌል ዘይነብብ ቃለ በከመ ረከበ ያገብኡ ሎቱ በዕለተ ደይን ከመ ይኰንንዎ[፩] ፤ ወዓዲ ይቤ እስመ እምቃልከ ትጸድቅ ወእምቃልከ ትትኴነን፤ ወበእንተዝ ይደሉ ይኩን ዘምሉእ ኵሎ ሠናያተ::

፫. ወእመሰ ኢየአምር መጽሐፈ ይኩን ማእምረ ወለባዌ፤ ወይኩን ዘእማዕከላይ ብእሲ ::

፬. ወእመሰ ንስቲት ሀገር ይእቲ ወኢተረክበ በውስቴታ ዘይደልዎ ጽጽስና፣ ወተረክበ እምንኡሳን ማእምር ወጠቢብ ዘኀዳጥ ዓመታቲሁ ወስምዐ ኮኑ ሎቱ እለ የአምርዎ ከመ ይደልዎ ይሠየም ኤጲስ ቆጶሰ

፩. ስለ ኤጲስ ቆጶስም፣ ለአብያተ ክርስቲያናት ሁሉ ኤጲስ ቆጶስ ሆኖ የሚሾመው የምእመናን ጠባቂ ነውር የሌለበት፣ ንጹሕና ቸር፣ የዚህንም ዓለም ጭንቀት የማያስብ፣ ፶ ዓመት የሞላው፣ የጐልማሳነት ኀይልን ያለፈ፣ ነገር የማይሠራ፤ በወንድሞችም መካከል ሐሰትን የማይናገር ይሆን ዘንድ እንደሚገባው በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ዘንድ ሰማን::

፪. ወንጌል ነገርን እንዳገኘ የሚናገር ሁሉ በፍርድ ቀን ይፈረድበት ዘንድ ይመለስለታል ብሏልና፣ ዳግመኛም ከቃልህ የተነሣ ትጸድቃለህ፣ «ከቃልህ የተነሣም ይፈረድ ብሃል» ብሏልና፤ ስለዚህም በጎውን ነገር ሁሉ የተመላ ይሆን ዘንድ ይገባል::

፫. መጽሐፍ የማያውቅ ቢሆን ግን ዐዋቂና አስተዋይ ይሁን፤ መካከለኛ ዕድሜም ያለው ሰው ይሁን::

፬. አገሪቱ ትንሽ ብትሆን፣ ግን በውስጧም ጵጵስና የሚገባው ባይገኝ ከታናናሾች እድሜው ጥቂት የሆነ አዋቂና ብልህ፤ የሚያውቁት ሰዎችም ኤጶስ ቆጶስነት ይሾም ዘንድ

---

[፩] ማቴ. ፲፪ ፥ ፴፮-፴፯

ወለእመ ሐይወ እምንእሱ ፍጹመ በግብረ አበው ቅዱሳን ወየዋሃን ዘየሐውር በፍኖተ ርትዕ ዘምኩር በኵሉ ግብር ወስምዐ ኮኑ ላዕሌሁ ከመ ፍጹም ውእቱ ይሠየም በሰላም::

፭. እስመ ሰሎሞን እንዘ መጠነ ፲ወ፪ ዓመታቲሁ ነግሠ ላዕለ ሕዝበ እስራኤል[፪] ፤ወኢዮአስኒ ነግሠ አመ ኮነ ሎቱ ፯ ዓመተ[፫] ወኢዮስያስኒ በሳምኒት ዓም ነግሠ በጽድቅ[፬]::

፮. እስመ እግዚአብሔር ነበበ በአፈ ኢሳይያስ ነቢይ ወይቤ ኀበ መኑ እኔጽር ዘእንበለ ኀበ የዋህ ወትሑት ወጽምው ዘይርዕድ እም ቃልየ[፭] ::

፯. ወካዕበ ይቤ ወንጌል «ብፁዓን የዋሃነ ልብ እስመ እሙንቱ ይወ ርስዋ ለምድር»::

፰. ወይኩንኬ መሐሬ፣ እስመ ይቤ ብፁዓን መሐርያን፣ እስመ እሙንቱ ይትመሐሩ[፮] ::

፪. ፩ኛ ነገሥ. ፫ + ፰
፫. ፪ኛ ዜና መዋ. ፳፬ + ፩
፬. ፪ኛ ነገሥ. ፳፪ + ፩ – ፪
፭. ኢሳ. ፷፯ + ፪
፮. ማቴ. ፭ + ፭

እንዲገባው ቢመሰክሩለት ከሕፃንነ ቱም ጀምሮ በቅዱሳንና የዋሃን አበው ሥራ ፈጽሞ ቢኖር በቀና መንገድም ቢሄድ በሥራው ሁሉ የተፈተነ ቢሆን ፍጹም እንደ ሆነም ቢመሰክሩለት በሰላም ይሾም::

፭. ሰሎሞንም ዕድሜው ዐሥራ ሁለት ዓመት ሳለ በእስራኤል ሕዝብ ላይ ነግሦ ነበርና፣ኢዮአስም ሰባት ዓመት በሆነው ጊዜ ገዥ ሆነ ተሾመ ፤ ኢዮስያስም በስምንት ዓመቱ በእውነት ነገሠ::

፮. እግዚአብሔር በነቢዩ በኢሳይ ያስ አንደበት እንዲህ ብሎ ተናግ ሮአልና፣ «ከቃሌ የተነሣ ወደሚ ፈራ የዋህ፣ ትሑትና ትዕግሥ ተኛ ወደሚሆን ነው እንጂ ወደ ማን እመለከታለሁ?

፯. ዳግመኛም ወንጌል እንዲህ ይላል "የዋሆች ብፁዓን ናቸው፤ እነርሱ ምድርን ይወርሳሉና»::

፰. የሚምር ይሁን፤ "የሚምሩ ብፁዓን ናቸው፤ እነርሱም ይማ ራሉ" ተብሏልና::



፱. ወይኩን እንከ ገባሬ ሰላም፤ እስመ ይቤ ብፁዓን ገባርያነ ሰላም፤ እስመ እሙንቱ ውሉደ እግዚአብሔር ይሰመዩ"[፯] ::

፲. ወይኩን እንከ ንጹሐ ልብ ዘእንበለ ቂም ወእከይ ወዐመፃ፣" እስመ ይቤ ብፁዓን ንጹሓነ ልብ፣ እስመ እሙንቱ ይሬእይዎ ለእግ ዚአብሔር" ፤

፲፩. ወይኩን እንከ መንፈሳዌ ትጉሀ ለገቢረ ሠናይ ዘኢስሱዕ ወኢመዓትመ፣ ወኢሰካሬ፣ ወኢ መስተበቅለ ዘአልቦ ጽልእ ወጋዕዝ ወኢዝትር፣ ወኢመፍቀሬ ወርቅ፣ ወኢጸዓሌ፣ ወኢይትዐበይ እንከ ከመ ኢይደቅ ውስተ መሥገርተ ሰይጣን እስመ ኵሉ ዘአዕበየ ርእሶ የኀሥር ወዘአትሐተ ርእሶ ይከ ብር[፰] ::

፲፪. ወከመዝ ይሠየም ኤጲስ ቆጶስ ዘአሐተ ብእሲተ አውሰበ፣ ዘይክል ሠሪዐ ቤቱ በሠናይ፣መምህር ወመገሥፅ ዘአልሐቀ ደቂቆ በንጽሕ[፱]::

፯. ማቴ- ፭ +፯
፰. ፩ኛ ጢሞ. ፫+፪–፯ ፤ ሉቃ. ፲፰+፲፱
፱. ቲቶ ፩ + ፯

፱. ሰላምን የሚያደርግ ይሁን "ሰላ ምን የሚያደርጉ ብፁዓን ናቸው፤ እነርሱ የእግዚአብሔር ልጆች ይባ ላሉ " ተብሏልና::

፲. ቂም፣ ክፋትና ዐመፅ የሌለበት ልበ ንጹሕ ይሁን፤ ልበ ንጹሖች ብፁዓን ናቸው እነርሱ እግዚአብ ሔርን ያዩታል ተብሏልና ::

፲፩.በጎ ሥራን ለመሥራት ትጉህ መንፈሳዊ ይሁን የማይሳሳ፣ የማ ይቆጣ ፣ የማይሰክር ፣ የማ ይበቀል፣ ጸብና ክርክር የሌለው፣ የማይኮራ፣ ገንዘብ የማይወድ፣ የማይሳደብ ይሁን፣ በሰይጣን ወጥመድ እንዳይወድቅ ፣ አይ ታበይ፣ ራሱን ከፍ ያደረገ ይዋ ረዳልና፣ ራሱንም ያዋረደ ይከብ ራልና ::

፲፪. እንደዚህ ያለ ኤጲስ ቆጶስ አንዲት ሴት ያገባ ቤተሰቦቹን በመልካም ማስተዳደር የሚችል ፣ የሚያስተምርና የሚመክር ልጆቹን በንጽሕና ያሳደገ ይሾም::

፲፫. ወብእሲቱሂ ትኩን መሐይምንተ እንተ ተሐፅን ደቂቃ በሠናይ አምልኮ ወፈሪሀ እግዚአብሔር፣ ወርቱዕ ለኤጲስ ቆጶስ ይትአዘዙሎቱ ሰብአ ቤቱ በትሕትና ወበፍርሀት፣ ወውእቱኒ ይኩን ዘአልቦ ነውር በትካዘ ዝ ዓለም ወበሥጋሁ፣እስመ ጽሑፍ ይፍትኖ ወያመክሮ እመ ውእቱ ዘአልቦ ነውር ወኢይኩን መዓትመ ከመ ይብል ጥበብ እስመ መዓትም ብእሲ ጠቢበ የሀጉል[፲] አላ ይኩን መሓሬ ወመጽዋቲ፣ እስመ ይቤ እግዚእነ በዝንቱ የአምሪክሙ ኵሉ ከመ አርዳእየ አንትሙ ለእመ ተፋቀርክሙ በበይናቲክሙ[፲፩]::

፲፫. ሚስቱም የምታምን፣ ልጆቿንም በመልካም አምልኮና እግዚአብሔርን በመፍራት የምታሳድግ ትሁን፤ ለኤጲስ ቆጶሱም ቤተሰቦቹ በትሕትናና በፍርሃት ይታዘዙለት ዘንድ ይገባል፤ እርሱም በዚህ ዓለም ጉዳይና በሥጋው ነውር የሌለበት ይሁን፤ ነውር የሌለበት እንደሆነ ፈጽመህ መርምረው ተብሎ ተጽፎአልና ፤ የማይቈጣ ይሁን፤ መጽሐፈ ጥበብ «ቍጣ ጥበበኛ ሰውን ያጠፋል» ብሏልና፤ ነገር ግን የሚራራና የሚመጸውት ይሁን፤ ጌታችን «እናንተ እርስ በርሳችሁ ብትዋደዱ ደቀ መዛሙርቴ እንደሆናችሁ ሁሉ በዚህ ያውቃችኋል» ብሏልና::

፲፬. ይኩንኬ መፍቀሬ ሰብእ፣ ዘይትዌከፍ ነግደ፣ ዘኢይነሥእ ገጸ መበይነ፣ ዘኢያደሉ ለባዕል ወለነዳይ፣ ዘቦ ኪን ዘይሰፍሕ እዴሁ ለውሂብ ፣ ዘይትዌከፍ መዓስበ መፍቀሬ ነዳያን ወዕጓለ ማውታ፣ ወመበለታት፣ ወዓዲ ይሴሲ ለእለቦን ደቂቅ ::

፲፬. ሰውን ወዳጅ፣ እንግዳን የሚቀበል፤ ፊት አይቶ የማያዳላ፣ ለባለጸጋና ደሃ የማያዳላ፣ ፈራጅ፣ ጥበብ ያለው፤ ለመሥጠት እጁን የሚዘረጋ፣ ረዳት የሌለውን የሚቀበል፣ ድሆችን፣ ደሀ አደጎችንና ባልቴቶችን የሚወድ ይሁን፤ ዳግመኛም ልጆች ያሏቸውን ይመግብ፤

፲. ምሳ. ፲፭ + ፲፰
፲፩. ዮሐ. ፲፫ + ፴፭



፲፭. ወእመሰ ቦ ብእሲ ሀካይ ወአኅለቀ ኵሎ ንዋዮ በስካር ወዝሙት፣ ወይፈቅድ ይመጽውትዎ ፣ ኢየሀቦ ኤጲስ ቆጶስ ትካዞ፤ወኢያብሖ ይባእ ቤተ ክርስቲያን፤ እስመ ይብል መጽሐፍ ለእለ ይገብሩ ከመዝ እስከ ማእዜኑ ሀካይ ትሰክብ ወማእዜ እምንዋም ትነቅሕ? ሕቀ ትነውም፣ወሕቀ ትነብር ሕቀ ትጴቅስ፤ ወሕቀ ታስተጋብእ እዴከ ዲበ እንግድዓከ፤ ወእምዝ ይመጽአከ ከመ እኩይ ሐዋርያ ንዴት ወተጽናስ ከመ ኄር ረዋዒ[፲፪]::

፲፭.ገንዘቡን ሁሉ በስካርና በዝሙት የጨረሰ ሰነፍ ቢኖር ግን፣ ሊመጸውቱትም ቢወድ፣ኤጲስ ቆጶሱ ግዳጁን አይስጠው፤ወደ ቤተ ክርስቲያንም ይገባ ዘንድ አይፍቀድለት፤ እንደዚህ ለሚሠሩ መጽሐፍ እንዲህ ይላልና ፣ «ሰነፍ እስከመቼ ድረስ ትተኛለህ? መቼስ ከእንቅልፍህ ትነቃለህ? አንድ ጊዜ ትተኛለህ ፤ አንድ ጊዜ ትቀመጣለህ፤ አንድ ጊዜ ታንቀላፋለህ፤ አንድ ጊዜ እጅህን በደረትህ ላይ ትሰበስባለህ፤ ከዚህ በኋላ ድህነት እንደክፉ መልእክተኛ ይመጣብሀል፤ ችጋርም እንደፈጣን ሯጭ ይደርስብሀል»::

፲፮.ኢርቱዕ ለኤጲስ ቆጶስ ከመ ይፍታሕ በአድልዎ ለገጸ ባዕል፤ ወይትኀየይ ነዳየ፤እስመ ይቤሎ እግዚአብሔር ለሙሴ ኢትፍታሕ በአድልዎ ለገጸ ባዕል ወኢትግምጽ ፍትሖ ለነዳይ እስመ ፍትሕ ለእግዚአብሔር ውእቱ፣ ወባሕቱ መፍትው ይፍታሕ በርትዕ::

፲፮. ኤጲስ ቆጶሱ ደኃውን ችላ ብሎ ለባለጸጋው ፊት በማድላት ይፈርድ ዘንድ አይገባውም፤ እግዚአብሔር ሙሴን «ለባለጸጋ ፊት በማድላት አትፍረድ፣ የድኃውን ፍርድም አታጓድል፤ ፍርድ የእግዚአብሔር ነው ብሏልና ፣ ነገር ግን በሚገባ ይፈርድ ዘንድ ይገባዋል::

፲፯. መፍትው ይኩን ሲሳዩ ለኤጲስ ቆጶስ መብልዐ ጥዑመ በአቅም ከመ ይክሃል ምህሮ ወገሥጾ ለሕዝብ ወይሚጦሙ ለኀበ እግዚአብሔር ወይርኀቅ እምኵሉ እኩይ ወያንብብ መጻሕፍተ ኵሎ ጊዜ::

፲፯. የኤጲስ ቆጶስ ምግቡ የጣመ፡ የላመ ይሁን፣ መጥኖ ይመገብ፤ ሕዝቡን መክሮ አስተምሮ ወደ እግዚአብሔር መመለስ ይቻለው ዘንድ፣ ከክፉም ሁሉ ይርቅ ዘንድ መጻሕፍትን ሁል ጊዜ ይመልከት ::

፲፪. ምሳሌ ፯ + ፱–፲፩

፲፰. ወይኩን መፍቀሬ ጥበብ ከመ ይክሃል ተርጕሞ መጻሕፍት በመንፈስ ቅዱስ ፣ ቃለ ወንጌል ኦሪተ ወነቢያተ በከመ ይቤ እግዚ አብሔር ለብዉ ቃለ መጻሕፍት እስመ እሙንቱ ስምዕ በእንቲአየ[፲፫] ::

፲፱. ወይደልዎ ለኤጲስ ቆጶስ የሐሊ ተኃሥሦ ወአገንጽሎ መጻሕፍት በበመትልው፣ ወያጽግቦሙ ለሕዝብ ትምህርተ መንፈሳዌ ወያርውዮሙ እምብርሃነ ሕጉ ለእግዚአብሔር በብዙኅ ተግሣጽ::

፳. ይቤ እግዚአብሔር አብርሁ ብርሃነ ጥበብ ላዕሌክሙ እስመ ጊዜሁ ውእቱ[፲፬] ::

፳፩. ከመዝኬ ርቱዕ ለኤጲስ ቆጶስ ይሕምም ወይጻሙ ወይትጋደል በእንተ ጽድቅ፤ወፈድፋደሰ በቅድመ ሕዝብ፡ ከመ ይርአዩ ግብሮ ወይትወከፉ ተግሣጾ ::

፳፪. ወዓዲ ውእቱሰ ኢይትሀከይ መነሂ፤ ወኢይትዐረክ ምስለ ዐቢያን፤ወኢይኩን ዘክልኤ ልቡ ወዘክልኤ ልሳኑ

፲፰. በመንፈስ ቅዱስ መጻሕፍትን መተርጐም ይችል ዘንድ ጥበብ መንፈሳዊን የሚወድ ይሁን ፤ የወንጌልን ቃል ኦሪትን ነቢያትንም መተርጐም ይችል ዘንድ እግዚአብሔር እንዳለ የመጻሕፍትን ቃል አስተውሉ እነሱ ስለ እኔ ነገር ምስክሮች ናቸውና::

፲፱. ለኤጲስ ቆጶስ መመራመርና መጻሕፍትንም ዘወትር መመልከትን ያስብ ዘንድ ይገባዋል፣ ለሕዝቡም መንፈሳዊ ትምህርትን ያጥግባቸው፤ ከእግዚአብሔር ሕግ ብርሃንነት የተነሣም በብዙ ምክር ያርካቸው ::

፳.እግዚአብሔር ጊዜው ነውና የጥበብን ብርሃን በእናንተ ላይ አብሩ አለ ::

፳፩. ለኤጲስ ቆጶስ እንደዚህ መከራ ሊቀበል፣ ሊደክምና ስለጽድቅም ሊጋደል ይገባዋል፤ ይልቁንም በሕዝቡ ፊት፣ ምክሩን ይቀበሉ ዘንድ ሥራውን ሊያሳያቸው ይገባል::

፳፪. እሱ ማንንም ቸል አይበል፤ ከታላላቆች ጋርም አይወዳጅ፤ ሁለት ልብና ሁለት አንደበት ያለው

፲፫. ዮሐ. ፭ + ፴፱
፲፬. ሆሴዕ ፲ + ፲፪



ወኢይትሉ መኳንንተ ፤ ወይፍራህ እግዚአብሔርሃ፤ ወኢይስማዕ ውዴተ በሐሰት ላዕለ ካልእ ወኢይትሀከይ ጸዊመ፤ ወኢያመክኒ ለበሊዕ፤ ወኢይ. በል በዓል ዮም በከመ ይገብሩ አሕዛብ ለበሊዕ ወሰትይ ወለፈጊዕ ::

፳፫. አላ ያሰስል እምኔሁ ኵሎ ፍትወተ ጽሩዐ ዘአልቦ ባቍዕ፤ እስመ ዝንቱ ኵሉ ምኑን ወጽሉእ በኀበ እግዚአብሔር ወፍቁር በኀበ አጋንንት::

፳፬. ይደልዎ ለኤጲስ ቆጶስ የአዝዞሙ ወይገሥጾሙ ለሕዝብ ያዕትት እምላዕሌሆሙ ዘንተ ኵሎ ምግባረ አላ ባሕቱ ይምሀሮሙ ወይገሥጾሙ፣ ወይሚጥሙ ይትመሰሉ ኪያሁ፤ ወይትልዉ ፍኖቶ በርትዕ፣ እስመ ይቤሎሙ እግዚ አብሔር ለደቂቀ እስራኤል "ዕቀቡ ሕግየ ወሥርዐትየ ወትእዛዝየ[፲፭]"፤ ወለሊሁ እግዚእነ ወአምላክነ ኢየሱስ ክርስቶስ አቅደመ ኵሎ ገቢረ ወመሀረነ ንትመሰል ኪያሁ ::

፳፭. ወበእንተዝ ይብል እስመ ዘይሜህር ወይገብር ዐቢየ ይከውን በመንግሥተ ሰማያት[፲፮]::

አይሁን፤ መኳንንቱንም አይከተል፤ እግዚአብሔርን ይፍራ፤ በሌላውም ላይ በሐሰት ነገር ሥራን አይስማ፤ ጾምንም ቸል አይበል፤ ለመብላትም ምክንያት አያድርግ፤ አሕዛብ ለመብላት ለመጠጣት፤ ተድላ ደስታ ለማድረግ በአልን ምክንያት እንዲያደርጉ «ዛሬ በዓል ነው እንብላ» አይበል::

፳፫. ነገር ግን ጥቅም የሌለው የስንፍና ምኞትን ከእርሱ ያርቅ፤ ይህ ሁሉ በእግዚአብሔር ዘንድ የተጠላ በአጋንንት ዘንድ የተወደደ ነውና ::

፳፬. ለኤጲስ ቆጶስ ይህንን ሁሉ ሥራ ከእነርሱ ያርቅ ዘንድ ሊያዝዛቸውና ሊመክራቸው ይገባዋል፤ነገር ግን እሱን ይመስሉ ዘንድ፣ አካሄዱንም በቅንነት ይከተሉ ዘንድ ይገስጻቸውና ያስተምራቸው እንጂ፣ እግዚአብሔር የእስራኤልን ልጆች ሕጌን ሥርዓቴንና ትእዛዜን ጠብቁ ብሎአቸዋልና፤ እሱ ጌታችን አምላካችን ኢየሱስ ክርስቶስም በጎ ሥራን ሁሉ አስቀደመ፤ እርሱንም እንመስል ዘንድ አስተማረን ::

፳፭. ስለዚህም የሚያስተምረውን የሚሠራ ሰው በመንግሥተ ሰማያት ታላቅ ይሆናልና ይላል ::

፲፭. ዘዳግ. ፮+፲፩
፲፮. ማቴ. ፭+፲፱

፳፮. ርቱዕ ለክሙ ለኤጲስ ቆጶሳት ትምህርምሙ ለሕዝብ ወታድኅንምሙ እምስሕተት በከመ ጸገወክሙ ለክሙ ክርስቶስ ።

፳፯. እስመ እግዚአብሔር ነበበ በአፈ ሕዝቅኤል ነቢይ ወይቤ ወልደ እጓለ እመሕያው ሰብአ ዐይን ረሰይኩከ ለቤተ እስራኤል ከመ ትስማዕ ቃለ እምአፉየ ወትገሥጾሙ በቃልየ ።

፳፰. ወእምከመ እቤሎ ለኃጥእ ሞተ ትመውት ወእመ ኢነገርኮ ለኃጥእ ወኢገሠጽኮ ከመ ይነስሕ ወይትመየጥ እምፍኖቱ እኩይ ወይሕየው ፣ ውእቱኒ ኃጥእ ይመውት በኀጢአቱ ወደሞ እትኀሠሥ እምኔከ ይቤ እግዚአብሔር።

፳፱. ወእመሰ ገሠጽኮ ለኃጥእ ወኢተመይጠ እምኀጢአቱ ይመውት በጌጋዩ፤ ወአንተሰ ታድኅን ነፍሰከ ።

፴. ወእመ ተመይጠ ጻድቅ እምጽድቁ ወገብረ ኀጢአተ እንዘ አርእዮ መቅሠፍትየ ቅድመ ገጹ ወኢገሠጽኮ ሞተ ይመውት

፳፮. ኤጲስ ቆጶሳት ሕዝቡን አስተምራችሁ ከስሕተት ታድኖአቸው ዘንድ ለእናንተ ይገባል፤ ክርስቶስ ለእናንተ እንደሰጣችሁ መጠን።

፳፯. እግዚአብሔር በነቢዩ በሕዝቅኤል ቃል የሰው ልጅ ሆይ! ቃሌን ከእኔ አፍ ሰምተህ በቃሌ ትገሥጻቸውና ትመክራቸው ዘንድ ለእስራኤል ወገኖች ጉበኛ አደረግሁህ » ብሎ ተናግሮአልና ።

፳፰. እግዚአብሔርም አለ፣ ኃጥኡን ሞትን ትሞታለህ ባልሁት ጊዜ፣ ንስሓ እንዲገባና ከክፉ መንገዱ እንዲመለስ ባትነግረውና ባትገሥጸውም ያም ኃጥእ በኃጢአቱ ሳለ ቢሞት ደሙን ከአንተ እፈልጋለሁ ይላል እግዚአብሔር።

፳፱. ኃጥኡን ግን መክረኸውና ገሥፀኸው ሳይመለስ በበደሉ እንዳለ ቢሞት አንተ ነፍስህን አዳንክ።

፴. ጻድቁም ከጻድቅነቱ ወጥቶ ኀጢአትን ቢሠራ በፊቱ መቅሠፍቴን እያሳየሁት በበደሉ እንዳለ ይሞት ዘንድ ባትመክረው ፣ ባትገሥፀውም



በጌጋዩ ፤ ወኢይዜከር ጽድቆ ዘገብረ ውእቱ ወእትኀሠሥ ደሞ እምእዴከ፤

፴፩. ወእመኒ ገሠጽኮ ለጻድቅ ከመ ኢየአብስ ወኢአበሰ ውእቱኒ ጻድቅ ሕይወተ የሐዩ፤ ወአንተኒ አድኅንከ ነፍሰከ[፲፯] ።

፴፪. ከማሁኬ ሶበ ይከውን ቀትል ወጸብእ ማዕከለ ሕዝብ እሙንቱ የኀሥሡ ሰብአ ዐይን ዘይዜንዎሙ ከመ ይትዐቀቡ፣ ወእመሰ ኢቀደመ ነጊሮቶሙ ከመ ይድኅኑ እምቀትል ደሙ እምላዕለ ርእሱ፤ እስመ ኢሰምዑ ቃለ ቀርን ።

፴፫. ወባሕቱ ዘሰ ርእየ ኲናተ እንተ ትመጽእ ላዕለ ብሔር ወይነፍሕ በቀርን ትእምርተ ለሠራዊት ወሰምዐ ዘይሰምዕ ቃለ ቀርን ወኢተግኀሠ ወመጽአ ኲናት ወረከበቶ ይገብእ ደሙ ላእለ ርእሱ፣ እስመ ሰምዐ ቃለ ቀርን ወኢተግኀሠ ወደሙ ይሰወጥ ዲቤሁ፤ ወዝንቱሰ እስመ ተግሕሠ አድኀነ ነፍሶ[፲፰] ።

፲፯. ሕዝ. ፴፫ ፡ ፪ - ፱ ፣ ፫ ፡ ፲፯–፲፱

እርሱም ያደረገውን ጽድቁን አላስብለትም ደሙን ከአንተ እጅ እፈልጋለሁ።

፴፩. ጻድቁን ግን እንዳይበድል ብትገሥጸው ብትመክረው እርሱ ከሞት ይድናል፤ አንተም ነፍስህን አዳንህ ።

፴፪. እንደዚሁም በሕዝቡ መካከል ጦርነትና ውጊያ በተደረገ ጊዜ እነርሱ ይጠበቁ ዘንድ የሚነግራቸው ጉበኛን ይፈልጋሉ፣ ከሞት ይድኑ ዘንድ፣ ባይነግራቸው ግን ደሙ በራሱ ላይ ነው የመለከት ድምጽን አልሰሙምና።

፴፫. ነገር ግን በሀገር ላይ የምትመጣ ጦርን ያየ ለሠራዊቱ ምልክት መለከትን ቢነፋ፣ የመለከቱን ድምፅ ሰምቶ ገለል ባይል፣ ጦርም መጥታ ብታገኘው፣ ደሙ በራሱ ላይ ነው ፤ የመለከቱን ድምፅ ሰምቶ ገለል አላለምና ደሙ በላዩ ላይ ይመለሳል፤ እርሱ ግን ገለል ብሏልና ነፍሱን አዳነ።

፴፬. ከማሁ ውእቱ ኤጲስ ቆጶስ ለእመ መሀረ ቃለ ሕይወት ይረ ክብ ሕይወተ ዘለዓለም፤ወኩናትሰ ኵነኔ ው እቱ ዘለዓለም ፤ ወቃለ ቀርንኒ ወንጌል ቅዱስ፤ ወሰብአ ዐይንሂ ኤጲስ ቆጶስ ውእቱ ለቅ ድስት ቤተ ክርስቲያን፤ መፍትው ለኤጲስ ቆጶስ ይርዐይ ወይምሀር ወያጽንዕ ቃለ መጻሕፍት ወያፍ ርህ በእንተ ኵነኔ፤ ወበእንተዝ ይገሥጾሙ ለእለ የሐውሩ ዘእንበለ አእምሮ፣ ወያርእዮሙ ክሡተ፤ ወለ እለ ኢየአምሩ ይምሀሮሙ ፤ ወለ እለ የአምሩ ያጽንዖሙ፤ ወለእለ ተገድፉ ያስተጋብኦሙ፤ ወይንግ ሮሙ ኵሎ ጊዜ በእንተ መድ ኀኒቶሙ ከመ ሶበ ሰምዑ ዘንተ ተግሣጸ ይግበሩ ሠናየ፡፡

፴፭. እስመ ይቤ እግዚአብሔር በነቢይ አስምዕ ላዕለ ዝንቱ ሕዝብ ወንግሮሙ ኀጢአቶሙ ለእመ ይትመየጡ ወይኔስሑ ወይድኀኑ እምጌጋዮሙ[፲፱]፡፡

፴፮. ወዓዲ ይቤሎሙ ሙሴ ለሕ ዝብ ስማዕ እስራኤል እግዚአ ብሔር አምላክከ ፩ ውእቱ[፳]፡፡

፴፬. እንደዚሁም ኤጲስ ቆጶሱ የሕይወትን ቃል ወንጌልን ቢያስተ ምር የዘለዓለም ሕይወትን ያገኛል፤ ጦሩም የዘለዓለም ፍዳ ነው፤ የመ ለከቱም ድምፅ ቅዱስ ወንጌል ነው ፤ ጉበኛ ሰላዩም የቅድስት ቤተ ክርስቲያን ኤጲስ ቆጶስ ነው፣ ኤጲስ ቆጶሱ ስለ ፍርድም እያስ ፈራ ቃሉንም እያጠና ያስተምርና ይጠብቅ ዘንድ ይገባዋል ፤ ስለዚህም ነገር ባለማወቅ የሚኖሩትን ሰዎች ይምከራቸው፤ ገልጾም ያስረዳቸው፤ የማያውቁትን ያስተምራቸው፤ የሚ ያውቁትንም ያጽናቸው፤ የተበተኑት ንም ይሰብስባቸው፤ ሁልጊዜም ስለድኅነታቸው ይንገራቸው ፣ ይህን ተግሣጽ በሰሙ ጊዜ በጎ ሥራን ይሠሩ ዘንድ ፡፡

፴፭. እግዚአብሔር በነቢዩ አድሮ በዚህ ሕዝብ ላይ አዳኝበታለሁ፤ ምን አልባት ከኀጢአታቸው ቢመለሱ ንስሐ ገብተውም ቢድኑ ኃጢአታ ቸውን ንገራቸው ብሏልና፡፡

፴፮. ዳግመኛም ሙሴ ሕዝቡን እስራኤል ሆይ ስማ ፈጣሪህ እግዚአብሔር አንድ ነው አላቸው አንድ እግዚአብሔር ነው፡፡

፲፱. ኤር. ፳፮ + ፫
፳. ዘዳግ. ፯ + ፳



፴፯. ወካዕበ ይቤ በወንጌል ቅዱስ ዘቦ እዝን ሰሚዐ ለይሰማዕ[፳፩]፡፡

፴፰. ወሰሎሞን ይቤ ስማዕ ወል ድየ ተግሣጸ አቡከ፤ ወኢትትሀየይ ትእዛዘ እምከ፤[፳፪] ወኢሰምዑ እስከ ዛቲ ዕለት፤ ወኀደግዎ ለእግ ዚአብሔር ለ፩ ዘበአማን አምላክ ርቱዕ ፡፡

፴፱. ወሰመዮሙ ትውልደ ዐላው ያን ወዘማውያን ዘአቅደምነ ነጊረ በእንቲአሆሙ፤ ወይእዜኒ አእምሩ ኦ ፍቁራኒነ እለ ተጠመቅሙ በሞቱ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስ ቶስ እስመ ኢርቱዕ የአብሱ እለ ነሥኡ ዘከመዝ ጸጋ፡፡

፵. አእምሩ አኀዊነ እስመ እምድ ኅረ ነሥኡ ጥምቀተ ሕይወት ወገ ብኡ ውስተ ግብረ ኀጢአት ይወ ርዱ ውስተ ኵነኔ ገሀነም ፡፡

፵፩. ወባዕዳንሂ እለ ኢኮኑ መሃይ ምናነ ወእምዝ አምኑ ወተጠምቁ ይከውኑ ብፁዓነ በቅድመ እግዚአ ብሔር፣ በከመ ይቤ እግዚእነ በወ ንጌል ቅዱስ «ብፁዓን አንትሙ ሶበ ይጼእሉክሙ፣ወይዘነጉጉክሙ፣ወ ይነቡ ኵሎ እኩየ ላዕሌክሙ እንዘ ይሔስዉ በእንቲአየ ተፈሥሑ እስመ ብዙኅ ውእቱ ዕሤትክሙ በሰማያት»[፳፫] ፡፡

፴፯. ዳግመኛም በቅዱስ ወንጌል ጆሮ ያለው መስማትን ይስማ አለ።

፴፰. ሰሎሞንም ልጄ፤ የአባትህን ተግሣጽ ስማ፣ የእናትህንም ትእ ዛዝ ቸል አትበል አለ፤ እነርሱ ግን በውነት የባሕርይ አምላክ የሚሆን አንድ እግዚአብሔርን ካዱት እንጂ እስከዚች ቀን ድረስ በሚገባ አልሰ ሙም፡፡

፴፱. አስቀድመን ስለእነርሱ የተና ገርንላቸው የሴሰኞች የወንጀለኞች ልጆች አላቸው፤ አሁንም በጌታ ችን በኢየሱስ ክርስቶስ በሞቱ በምትመሰል ጥምቀት የተጠመቃ ችሁ ወዳጆቻችን ሆይ፣ አስተውሉ፤ እንደዚህ ያለ ልጅነትን የተቀበሉ ሰዎች ይበድሉ ዘንድ አይገባምና፡፡

፵. ወንድሞቻችን ሆይ ዕወቁ፤ ካመኑ ከተጠመቁ በኋላ ወደ ኃጢአት ሥራ ቢመለሱ ወደ ገሀ ነም ፍርድ ይወርዳሉና፡፡

፵፩. ምእመናን ያልሆኑ ሌሎ ችም ከዚህ በኋላ ቢያምኑና ቢጠ መቁ በእግዚአብሔር ፊት ንዑዳን፣ ክቡራን ይሆናሉ፣ ጌታችን በወን ጌል ንዑዳን ክቡራን ናችሁ እን ዳለ፣ በእኔ ምክንያት ቢሰድቧ ችሁ ቢያሽሟጥጧችሁ የኔን ነገር ሀሰት ነው እያሉ በናንተ ላይ በተናገሩ ጊዜ ደስ ይበላችሁ፤ ዋጋ ችሁ በመንግሥተ ሰማያት ብዙ ነውና»፡፡

፳፩. ማቴ. ፲፩–፲፭
፳፪. ምሳ. ፩ + ፰
፳፫. ማቴ ፭ + ፲፩–፲፪

፵፪. ወእመሰ ቦ ዘነበበ ሐሰተ ላዕሌሁ ብፁዕ ውእቱ፤ እስመ ጽሑፍ ዘይብል ኵሉ ብእሲ ዘኢኮነ ምኩረ ኢኮነ ኅሩየ በኀበ እግዚአብሔር [፳፬] ::

፵፫. ወለእመ ቦ ዘወፅአ እምሕግ ወረገምዎ ለሊሁ ለርእሱ አምጽአ መርገመ፤ ከማሁ ንሕነኒ ለእመ ኢሰማዕነ ትእዛዛቲሁ ለእግዚአብሔር ወኢገበርነ ፈቃዶ ናመጽእ ላዕሌነ መርገመ ::

፵፬. ወዓዲ ንከውን ርኁቃነ እም እግዚአብሔር፤ እስመ ዘለሊሆሙ ይሜህሩ ኢይገብሩ[፳፭] ፤ ወኢይት መየጡ እምግዕዞሙ ::

፵፭. ኢመፍትው ለኤጲስ ቆጶስ ይገሥጾሙ ወያስተኀፍሮሙ ለእለ ይገብሩ ከመዝ፣ አላ ርቱዕ ይም ሀሮሙ በፍቅረ ክርስቶስ በከመ ይደሉ ለተቀንዮ::

፵፮. ርቱዕ ለኤጲስ ቆጶስ ይኅሥሥ ጽድቀ፤ ወኢያክብሮሙ ለዕ ልዋን፤ ወኢያድሉ በውስተ ፍትሕ ወኢይንሣእ ሕልያነ በኀበ

፵፪. ሰው አስትን በላዩ የተናገ ረበት ቢኖርም ብፁዕ ነው፤ «በመከራ ያልተፈተነ ሰው ሁሉ በእግዚአብሔር ዘንድ የተመረጠ አይደለም» የሚል ጽሑፍ አለና::

፵፫. ከሕግ ወጥቶም የረገሙት ሰው ቢኖር እርሱ ለራሱ ርግ ማንን አመጣ፣ እኛም እንደርሱ የእግዚአብሔርን ትእዛዞች ሰም ተን ፈቃዱን ባንፈጽም በላያችን ርግማንን እናመጣለን::

፵፬. ዳግመኛም ከእግዚአብሔር የተ ለየን እንሆናለን፤ እነርሱ የሚያ ስተምሩትን የማይሠሩ፣ ከልማ ዳቸውም የማይመለሱ ናቸውና::

፵፭. ለኤጲስ ቆጶሱ እንደዚህ የሚ ሠሩትን ይቈጣቸውና ያሳፍራ ቸው ዘንድ አይገባውም፣ነገር ግን ለአምልኮት እንደሚገባ በክርስቶስ ፍቅር ያስተምራቸው እንጂ ::

፵፮. ለኤጲስ ቆጶሱ እውነትን ይመረምር ዘንድ ይገባዋል፤ ከሃድ ያንንም አያክብራቸው፤ በፍርድ ጊዜም አያድላ፤ ከማንም መማለ

፳፬. ያዕ. ፩+፲፫ ፣ ዕብ. ፲፪+፳
፳፭. ማቴ. ፳፫–፫



መኑሂ፤ እስመ ሕልያን የዐውር አዕይንቲሆሙ፤ ለጠቢባን፣ ወያ ጸንን ነገረ ፍትሕ ወርትዕ፤ ወዓዲ ቦ ኀበ ይብል አዕትቱ እምኔክሙ ኵሎ እኩየ[፳፮]::

፵፯. ወሰሎሞንሂ ይቤ ኀበ መካን እንተ ግዕዙ ኢትሑር ህየ፣ ተገ ኀሥ እምኔሆሙ ወተመየጥ እስመ ኢይነውሙ እመ ኢገብሩ እኩየ ወይርኅቅ ንዋም እምአዕይንቲ ሆሙ፤ ወኢይነውሙ ይበልዑ መብልዐ ኀጢአት ::

፵፰. ወእመሰ ኢለበወ ኤጲስ ቆጶስ ወሖረ በትምይንት፣ወመ ናኔ ኮነ በከመ ገብረ ሳኦል ለአጋግ[፳፯]፤ ወኤሊ ካህን ዘኢገ ሠጾሙ ለደቂቁ እለ ኀደጉ ትእዛዘ እግዚአብሔር[፳፰]፣ ወናሁ ከመውእቱ ለሊሁ ሀጕለ ክብሮ፤ ወዓዲ ደብተራሁ፤ ቅድስተ ዘህገሩ ወገብረ ዓመፃ በቅድመ፣

ጃን አይቀበል፤ መማለጃ መቀበል የአዋቂዎችን ዓይኖች ያሳውራ ልና፤ የቀናውን የፍርድ ነገርም ያጣ ምማልና፣ ዳግመኛም ክፋትን ሁሉ ከእናንተ አርቁ የሚል አንቀጽ አለና ::

፵፯. ሰሎሞንም እንዲህ አለ «እነ ርሱ በተጓዙበት ቦታ ወደዚያ አት ሂድ፤ ከእነርሱም ፈቀቅ በል ተመ ለስም፤ክፉ ካላደረጉ አይተኙምና ከዓይኖቻቸውም እንቅልፍ ይወገ ዳል፤ አይተኙምም የኃጢአትን መብል ይመገባሉ ::

፵፰. ኤጲስ ቆጶሱ ባያስተውል በተንኰልም ቢሔድ ፣ ሳኦልም በአ ጋግ እንደ አደረገ፣ ካህኑ ኤሊም የእግዚአብሔርን ትእዛዝ የተዉ ልጆቹን እንዳልገሠጻቸው፣ እንደ ካህኑ ኤሊ ናቂ ቢሆን እነሆ እርሱ ክብሩን ያጣል፤ ዳግመኛም የሀገ ሩን ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ያጣል፣

፳፮. ዘፀ. ፳፫ + ፯ – ፰
፳፯. ፩ኛ ሳሙ. ፲፭–፴፬
፳፰. ፩ኛ ሳሙ. ፪+፳፬–፳፰፤ ፬+፲–፲፩

እግዚአብሔር፣ ወኮነ ዕቅፍተ ወመስትተ ለሐዲስ ተክል ለእለ ነሥኡ ጥምቀተ ወዓዲ ለንኡሰ ክርስቲያን ለዕድ ወለአንስት ከማሁ ክመ::

፺፱. ወእመሰ ኢመሀረ፣ወኢገሠጸ፣ ወኢሖረ በፍኖተ ርትዕ፣ ወኀደገ ትእዛዛቲሁ ለእግዚአብሔር፣ ወበእንተዝ ይረክብ ግዘተ፤ ወይመጽእ ላዕሌሁ መቅሠፍተ እግዚአብሔር ፣ እስመ አስሐተ ፍኖቶሙ ለሕዝብ በከመ ስሕቱ ሕዝብ ዘበመዋዕለ ኢዮርብአም[፷፱]:: ወእለ ተቀትሉ ምስለ ቆሬ[፸]::

፻. ወእመሰ ቦ ዘይኤብስ ዲበ ኤጰስ ቆጰስ ወላዕለ ሥዩማን እንዘ አልቦሙ አበሳ ወንጹሓን እሙንቱ፤ ኢይደልዎ ይባእ ቤተ ክርስቲያኑ ለእግዚአብሔር፣ እስመ ደፈረ ወሖረ በእበድ በፍትወተ ነፍሱ ::

፻፩. ወበእንተዝ ይረክብ ዘረከቦሙ ለእለ ተሣለቁ ላዕለ ኖኅ::[፸፩] ወበከመ አካን ዘነሥአ ለርእሱ ኅሩመ [፸፪]፤ ወበከመ ግያዝ ዘነሥአ ንዋየ እምኅበ ንዕማን ሶርያዊ [፸፫]::

በእግዚአብሔርም ፊት በደልን ይሠራል፣ ጥምቀትን ለተቀበሉ አዲስ አማኞችም እንቅፋትና መሰናክል ይሆናል፤ ለወንዶችና ሴቶች ንዑስ ክርስቲያንም ፈጽሞ እንዲሁ ነው ::

፺፱.ባያስተምርና ባይገሥጽ፣ በቅንነት መንገድም ባይሔድ፣ የእግዚአብሔርንም ትእዛዛት ቢተው፣ ስለዚህ ውግዘት ያገኛዋል፤ የእግዚአብሔር መቅሠፍት ይመጣበታል በኢዮርብአም ዘመን የነበሩ ሕዝብና ከቆሬ ጋር የተገደሉት እንደሳቱ የሕዝቡን መንገድ አሳስቷልና::

፻. በደል ሳይኖርባቸው ንጹሓንም ሲሆኑ በኤጲስ ቆጶሱ ላይ በሹማምንቱም ላይ የሚበድል ቢኖር ወደ እግዚአብሔር ቤተ ክርስቲያን ሊገባ አይገባውም፤ ደፍሮ በራሱ ፈቃድ በስንፍና ኖራልና::

፻፩. ስለዚህም በኖኅ ላይ የተሣለቁ ሰዎች ያገኛቸውን ያገኛል፤ እርም የሆነውን ለራሱ እንደወሰደ እንደ አካን፣ ከሶርያዊው ከንዕማንም ገንዘብ እንደ ተቀበለው እንደ ግያዝ ይሆናል::

፷፱ ፩ኛ.ነገ.፲፪.፳፱
፸. ዘኍ. ፲፮. ፵
፸፩ ዘፍ.፱. ፳-፳፭.
፸፪ ኢያ.፯.፩
፸፫.፪ኛ. ነገ. ፭. ፳፫



፻፪. ናሁኬ ይደልዎ ለኖላዌ አባግዕ ይምሀር ወይገሥጽ በየውሃት፤ ወይሚጦሙ ውስተ ንስሓ ጠዪቆ ለለአሕዱ አሐዱ በሕይወቶሙ፤ ወይሥራዕ ንብረቶሙ በከመ ይደሉ በሰላም ከመ ይሕየዉ ሕዝብ ሠናየ ሕይወተ፣ ወይትመየጡ እምኅጣውኢሆሙ፤ ዝኬ ሥሙር በቅድመ እግዚአብሔር፤ እስመ ሶበ ተመይጠ ሰብእ እምኅጢአቱ ፣ ወገብአ ውስተ ንስሓ ርእዮሙ ኪያሁ ይትሜሀሩ ካልኣን ሠናየ አምልኮ::

፻፫. ወበእንተዝ ይደልዎ ለኤጲስ ቆጰስ ይኩን ትጉሀ ለገቢረ ሠናይ ከመ ይትዐወቅ ግብሩ በኀበ ኵሉ እስመ መርሖሙ ወኖላዊሆሙ ለሊቃውንት ወለመኳንንት፣ ወለመምህራን ወለኵሎሙ ዘእምታሕቴሁ::

፻፬. መፍትው ለኤጲስ ቆጳሳት ይንበሩ ውስተ ቤተ ክርስቲያን ምስለ ካህናት፤ ወይፍትሑ ለለ አሐዱ አሐዱ በከመ ይደሉ፤ እስመ ሎሙ ወሀበ እግዚአብሔር ሥልጣነ፤ ወአዘዞሙ እንዘ ይብል «ዘአሰርክሙ በምድር ይኩን እሱረ በሰማያት፣ ወዘፈታሕክሙ በምድር ይኩን ፍቱሐ በሰማያት»[፸፬]::

፻፪. እነሆ የምእመናን ጠባቂያቸው በየውሃት ያስተምርና ይገሥጽ ዘንድ፣ እያንዳንዳቸውንም ተረድቶ በሕይወታቸው ወደ ንስሓ ይመልሳቸው ዘንድ ይገባዋል፤ ሕዝቡም መልካም ኑሮን እንዲኖሩ፣ ከኀጢአታቸውም እንዲመለሱ አነዋወራቸውን ያዘጋጅ ዘንድ ይገባዋል፤ ይህም በእግዚአብሔር ፊት የተወደደ ነው ፤ ሰው ከኀጢአቱ ተመልሶ ወደ ንስሓ ቢገባ ሌሎች እርሱን አይተው መልካም አምልኮትን ይማራሉና ::

፻፫. ስለዚህም ለኤጲስ ቆጳሱ ሥራው በሁሉ ዘንድ እንዲታወቅ መልካም ሥራን ለመሥራት ትጉህ ይሆን ዘንድ ይገባዋል፤ ለሊቃውንቱና ለመኳንንቱ፣ ለመምህራኑና ከበታቹ ላሉት ሁሉ መሪያቸውና ጠባቂያቸው ነውና::

፻፬. ኤጲስ ቆጳሳት ከካህናት ጋር በቤተክርስቲያን ተቀምጠው ለእያንዳንዱ እንደሚገባ ይፈርዱ ዘንድ ይገባል፤ እግዚአብሔር ለእነርሱ ሥልጣንን ሰጥቶአልና እንዲህም ብሎ አዝዞአቸዋልና «በምድር ያሰራችሁት በሰማይ የታሰረ ይሁን፤ በምድርም የፈታችሁት በሰማያት የተፈታ ይሁን»::

፸፬ ፡ ማቴ.፲፰.፲፰

፶፭. ርቱዕ ለኤጲስ ቆጶስ ይሚጠሙ ለሕዝብ ውስተ አእምሮ እግዚአብሔር ወይትወከፍ ንስሐሆሙ ለእለ ተመይጡ ኀበ እግዚአብሔር፤ ወይምህሮሙ ወይናዝዞሙ በተየውሆ ወበፍቅር፣ ወበፍሥሓ ልብ እስመ እግዚአብሔር አምላክ መሓሪ ውእቱ እስመ ይቤሎ እግዚአብሔር ለሕዝቅኤል ነቢይ::

፶፮. በሎሙ ሕያው አነ ይቤ አዶናይ እግዚአብሔር ከመ ኢይፈቅድ ይሙት ኃጥእ ዳዕሙ ከመ ይነስሕ ወይኅድግ ፍኖቶ እኪተ ወይሕየው»፤ ተመየጡ ተመየጡ፤እምፍኖትክሙ እኩይ፤ ወለምንት ትመውቱ ቤተ እስራኤል::

፶፯. ወአንተ ወልደ ዕጓለ እመሕያው በሎሙ ለደቂቀ ሕዝብከ ጽድቁ ለጻድቅ ኢያድኅኖ አመ ይጌጊ፣ ወኀጢአቱ ለኃጥእ ኢያሐምሞ አመ ይኔስሕ እምጌጋዩ፤ ወጻድቅኒ ኢይድኅን እምከመ አበሰ::

፶፰. ሶበ እቤሎ ለጻድቅ ሕይወተ ተሐዩ ለእመ ተአመነ በጽድቁ ወገብረ ኀጢአተ፣ ኵሎ ጽድቆ ኢይዜከር ሎቱ፣ በኀጢአቱ ዘገብረ ይመውት ::

፶፭. ኤጲስ ቆጶሱ ሕዝቡን እግዚአብሔርን ወደ ማወቅ ይመልሳቸው ዘንድ ወደ እግዚአብሔር የተመለሱትንም ንስሓቸውን ተቀብሎ በማለዘብ በፍቅርና በልብ ደስታ ያስተምራቸውና ያረጋጋቸው ዘንድ ይገባል፣ እግዚአብሔር መሓሪ አምላክ ነውና፤ እግዚአብሔር ለነቢዩ ሕዝቅኤል እንዲህ ብሎታልና::

፶፮. «እኔ ሕያው ነኝና ኀጢአተኛው ከመንገዱ ተመልሶ በሕይወት ይኖር ዘንድ እንጂ፣ ኀጢአተኛው ይሞት ዘንድ አልፈቅድም» ይላል ጌታ እግዚአብሔር፣ የእስራኤል ቤት ሆይ ተመለሱ፣ ከክፉ መንገዳችሁ ተመለሱ፤ ስለምንስ ትሞታላችሁ በላቸው ::

፶፯. አንተም የሰው ልጅ ሆይ፣ የሕዝብህን ልጆች እንዲህ በላቸው፣ «በበደለበት ቀን የጻድቅ ጽድቁ አያድነውም፤ኀጢአተኛም ከኀጢአቱ በተመለሰበት ቀን ኃጢአቱ አያሰናክለውም፣ ጻድቁም ኀጢአት ከሠራ በጽድቁ በሕይወት አይኖርም»::

፶፰. እኔ ጻድቁን በሕይወት ትኖራለህ ባልሁት ጊዜ እርሱ በጽድቁ ታምኖ ኀጢአት ቢሠራ በሠራው ኀጢአት ይሞታል እንጂ፣ ጽድቁን አላስብለትም::



፶፱. ወእምከመ እቤሎ ለኃጥእ ሞተ ትመውት ወነሰሐ እምኀጢአቱ ወገብረ ጽድቀ ወርትዐ::

፷. ወአግብአ አኀዘ፣ ወፈደየ ዘሄደ፣ ወበሕገ ሕይወት ሖረ፣ ወኢገብረ ኀጢአተ ሕይወተ የሐዩ፤ ወኢይመውት[፴፭] በኀጢአት ዘአበሰ ወኢይዜከር ሎቱ አባሳሁ ወጌጋዩ እስመ ገብረ ጽድቀ ወርትዐ ወቦቱ የሐዩ፤

፷፩. ወበእንተዝ ይሴፈዉ ኃጥኣን እምከመ ተመይጡ እምኀጣውኢሆሙ፤ ወነስሑ ይርከቡ ተስፋ ሠናየ፤ ወእሙንቱሰ ይወርስዋ ለምድር፤ ወእለ ኢአበሱ ይትዐቀቡ ከመ ኢይረዱ ውስተ ምንዳቤ ወብካይ ወኀዘን::

፷፪. አእምርኬ ወለቡ ኦ ሰብእ እመ አበስከ ወገበርከ ኀጢአተ በዝ ዓለም ወኢነሳሕከ አልብከ ሕይወት፤ ወነስሕ እንከ እንዘ ሕያው አንተ፤ እስመ እምድኅረ ሞት አልቦ ንስሓ በከመ ይቤ ዳዊት «እስመ አልቦ በውስተ ሞት ዘይዜከረከ ወበሲኦልኒ መኑ የአምነከ[፴፮] ::

፴፭ ሕዝ ፴፫ : ፲፩ - ፲፭
፴፮ መዝ. ፮ : ፭ - ፮

፶፱. እኔም ኀጢአተኛውን ሞትን ትሞታለህ ባልሁት ጊዜ እርሱ ከኀጢአቱ ተመልሶ ፍርድንና ቅን ነገርን ቢያደርግ፣

፷. እርሱም መያዣውን ቢመልስ፣ የነጠቀውንም ቢከፍል፣ በሕይወትም ሕግ ቢሄድ፣ ኀጢአትም ባይሠራ በሕይወት ይኖራል እንጂ በበደለው ኃጢአት አይሞትም፣ በደሉንም አያስብበትም፣ እውነትንና ርትዕን ሠርቶአልና በሕይወትም ይኖራል::

፷፩. ስለዚህም ኃጥኣን ከኀጢአቶቻቸው ተመልሰው ንስሓ ከገቡ መልካም ተስፋን ያገኙ ዘንድ ተስፋ ያደርጋሉ፤ እነርሱም ምድርን ይወርሷታል፤ ያልበደሉም ወደ መከራና ወደ ልቅሶ፣ ወደ ኀዘንም እንዳይወርዱ ይጠንቀቁ::

፷፪. ሰው ሆይ! ዕወቅ፣ አስተውልም፤ በዚህ ዓለም ብትበድል ኀጢአትንም ብትሠራ ንስሓም ባትገባ ድኅነት አይኖርህም፤ እንግዲህ በሕይወት ሳለህ ንስሐ ግባ፤ ዳዊት በሞት የሚያስብህ የለምና፣ በሲኦልም የሚያምንህ ማን ነው? ብሎ እንደ ተናገረ ከሞት በኋላ ንስሓ የለምና::

፳፫. ርቱዕኬ ኦ አኃዊነ ንንበር ድልዋኒነ በገቢረ ሠናይ፤ ወንሑር በፍኖተ ርትዕ እንተ አልባቲ ኀዘን፤ ንስማዕ እንከ ወንለቡ ዘይቤ ‹‹አርትዕ ፍኖትየ ወሑረ ትየ በከመ ነቢብከ››[፹፯] ወኢንኩን እንከ ሕፁፃነ እምኵሉ ምግባረ ሠናይ አላ ንዕቀብ ቃለ ቅዱሰ ዘይቤ ወንጌል ቅዱስ በእንተ ኃምስ ደናግል ጠባባት፤ ወአኮ ከመ ኃምስ አብዳት ደናግል እለ ኀልቀ እምኔሆን ቅብዕ ዘውእቱ ገቢረ ሠናይ ወወፅአ እምክብካብ ዘበሰማያት[፹፰]::

፳፬. ወበእንትዝ መፍትው ንዕቀብ ርእሰነ፤ ወንኩን ኬንያ ለርእስነ፤ ወንዕቀብ ጊዜሁ ለመርዓዊ ከመ ኢንድኅፅ ውስተ ኀጢአት፤ ወዘሰ ጽድቀ ይገብር ይዕቀብ ገቢረ ሠናይ እስከ ፍጻሜሁ::

፳፭.ወይደልዎ ለኤጲስ ቆጶስ ይለቡ ወይፍታሕ በርትዕ፤ እስመ ፍትሕ ለእግዚአብሔር ውእቱ ይገሥጾሙ ለኃጥኣን ይሑሩ ፍኖተ ርቱዐ፤ ወእም ከመ ተመይጡ ይትወከፍ ንስ ሓሆሙ በሣህል ወበምሕረት::

፹፯ መዝ ፻፲፰ - ፻፴፫
፹፰ ማቴ. ፳፭ - ፳

፳፫. ወንድሞቻችን ሆይ በጎ ሥራን በመሥራት ተዘጋጅተን እንኖርና ኀዘን በሌለባት በቅንነት መንገድ እንሄድ ዘንድ ይገባናል፤ ‹‹እንደ ቃልህ መንገዴንና አካሄ ዴን አቅና›› ያለውን እንስማ እና ስተውልም፤ እንግዲህ ወዲህም በጎ ሥራ ሁሉ የጎደለን አንሁን፤ ነገር ግን በጎ ሥራ የሆነው ዘይት ስላለቀባቸውና ከሰማያዊው ሰርግ ስለ ወጡት አምስት ሰነ ፎች ደናግል ሳይሆን፤ ስለ አም ስቱ ብልሆች ደናግል ቅዱስ ወን ጌል የተናገረውን ቅዱስ ቃል እን ጠብቅ::

፳፬. ስለዚህም እራሳችንን ከክፉ ነገር እንጠብቅ ዘንድ፣ ለራሳች ንም ብልሆች እንሆን ዘንድ፣ በኀጢአትም እንዳንሰነካከል መር ዓዊ የሚመጣበትን ጊዜ እንጠብቅ ዘንድ አግባብ ነው ፤ ጽድቅን የሚሠራ ግን እስከ ዕለተ ሞቱ ድረስ በጎ መሥራትን ይጠብቅ::

፳፭.ለኤጲስ ቆጶሱም በእውነት አስተውሎ ይፈርድ ዘንድ ይገ ባዋል፤ ፍርድ ለእግዚአብሔር ነውና፤ የቀና መንገድን ይሄዱ ዘንድ ኀጥአንንም ይምከራቸው፣ ያስተምራቸው፣ የተመለሱ እንደ ሆነም ንስሐቸውን· በይቅርታና በምሕረት ይቀበላቸው::



፳፮. ተዘከርኬ ዘይቤ እግዚእነ ይከ ውን ዐቢይ ፍሥሓ በሰማያት በእንተ ፩ ኀጥእ ዘይኔስሕ፣ [፹፱] ወእመሰ ኢተወከፍክሙ ለእለ ይኔስሑ ወገደፍክሙ ዘረውከ መርዔተከ፤ ወኢለበውከ ዘይቤ ዳዊት ኢትመጥዋ ለአራዊት ለነፍስ እንተ ትገኒ ለከ [፺]::

፳፯. እስመ ከመዝ ይቤ እግዚአብ ሔር ዘወድቀ ኢይትነሣእኑ ወዘስሕተ ኢይትመየጥኑ::

፳፰. በእንተ ምንት ዐለዉ ሕዝ ብየ ማዕሌተ እኩየ፣ ወአጽንዑ ምክሮሙ ወአበዩ ኀዲገ ኃጢ አት::

፳፱. አጽማዕኩ ይእዜኒ ወሰማ ዕኩ፤ አኮኑ ከመዝ ይቤሉ አልቦኑ ሰብእ ዘይኔስሕ እምእ ከዩ፣ ወይብል ምንተ ገበርኩ [፺፩]:: ተመየጡ ኦ ደቂቅየ እለ ርኁቅሙ ወአነ እፌውስ ቊስለክሙ::

፹፱. ሉቃ ፲፭ . ፯.
፺፩ መዝ. ፴፫ ፲፱
፺፩. ኤር. ፰ ፬.፮

፳፮.ጌታችን ‹‹ከኀጥኣን አንዱ ንስሐ ስለገባ በሰማይ ፍጹም ደስታ ይሆናል›› ያለውን አስብ፣ ንስሓ የገቡትን ባትቀበላቸውና ብትጥላቸው ግን መንጋዎችህን በተንህ፤ ዳዊትም የምትገዛልህን ሰውነት ለአራዊት አሳልፈህ አትስ ጣት ያለውን አላስተዋልህም::

፳፯.እግዚአብሔርም ‹‹የወደቀ አይ ነሣምን፣ የበደለስ አይመለስ ምን›› ብሎ እንደዚህ ተናግሯ ልና::

፳፰. ወገኖቼ ብዙ ወንጀልን ስለ ምን·ወነጀሉ? ምክራቸውንስ የኀ ጢአትን ሥራ መተውንስ እንቢ ብለው ስለ ምን ጸኑ?

፳፱.አሁንም ሰማሁ ፤ አዳመጥ ኩም፤ ከኃጢአት ወደ ጽድቅ፣ ከክፋት ወደ በጎነት የሚመለስ ሰው የለምን? ብሎ እንደዚህ ተናገሯልና ምንሠራሁ የሚል የለምን ከጽድቅ ከበጎ ሥራ የራቃችሁ ልጆቼ ሆይ ከኃጢአት ወደ ጽድቅ፣ ከክፋት ወደ በጎነት ተመለሱ፣ እኔም የኃጢአታችሁን ቊስል እፈውሳለሁ::

፸. ኦ ኤጲስ ቆጶስ ተወከፎሙ ለእለ ይኔስሑ ይትመየጡ ኀቤከ፤ ወኢትኩን ዘ፪ኤ ልቡ፤ ወኢታዕቢ ልበከ ከመ እለ አልቦሙ ምሕረት፤ እስመ ዘይገብር ከመዝ ኢይፈርሆ ለእግዚአብሔር፤ አላ ባሕቱ ሐሊ ትግበር ትካዘሙ በከመ ይደሉ።

፸፩.ንዕቀብ እንከ ርእሰነ ወኢንትሐወል ምስለ ኀጥኣን ወዐማፅያን እለ ይገብሩ ከመዝ፤ ጽድቁ ለጻድቅ ለርእሱ ወዘሰ ይገብር ኀጢአተ ዘእንበለ ሕግ ትገብእ ጌጋዩ ዲበ ርእሱ[፷፪]።

፸፪. እስመ ይቤ በሕዝቅኤል ነቢይ፤ ምድር ለእመ አበሰት ሊተ፤ ወስሕተት ወጌገየት አነሥእ እዴየ ላዕሌሃ ወእቀጠቅጥ ኀይለ እክል፤ ወእፌኑ ላዕሌሃ ረኃበ፤ ወአጠፍእ እምላዕሌሃ ሰብአ ወእንስሳ።

፸፫.ወለእመ ሀለዉ እሉ ፫ዕደው ማዕከለ፤ ኖኅ ወዳንኤል ወኢዮብ እሙንቱ ያድኅኑ በጽድቆሙ ነፍሶሙ ይቤ እግዚአብሔር አዶናይ።

፷፪. ሕዝ. ፲፰. ፳

፸. ኤጲስ ቆጶስ ሆይ ! ንስሓ ገብተው ወደ አንተ የተመለሱትን ሰዎች ተቀበላቸው፤ ሁለት ልብ አትሁን፤ ምሕረት እንደሌላቸው ሰዎች ልብህን አታሳብይ፤ እንደዚህ የሚያደርግ ሰው እግዚአብሔርን አይፈራውምና፤ ነገር ግን እንደሚገባ ግዳጃቸውን ታደርግላቸው ዘንድ ብቻ አስብ እንጂ።

፸፩.እንግዲህም ራሳችንን እንጠብቅ፤እንደዚህም ከሚያደርጉ ከኃጢአተኞችና ከዐመፀኞች ጋራ አንቀላቀል፤ የጻድቅ ጽድቁ ለራሱ ነው፤ ከሕግም ወጥቶ ኀጢአትን የሚሠራ በደሉ በራሱ ላይ ትመለሳለች።

፸፪.እግዚአብሔር በነቢዩ በሕዝቅኤል እንዲህ ብሏልና፤ ምድር ብትበድል ፤ ብትስስን ኀጢአትም ብትሠራ እኔ በላይዋ ላይ የመዓቴን እጅ እዘረጋለሁ፤ የእህልንም ኃይል አጠፋለሁ፤ ረኃብንም በላይዋ እሰድዳለሁ፤ ከእርሷም ሰውና እንስሳን አጠፋለሁ ብሏል።

፸፫.እሊህ ሦስቱ ሰዎች ኖኅ ዳንኤልና ኢዮብ በኀጥአን መካከል ቢኖሩ እነርሱ በጽድቃቸው ራሳቸውን ያድናሉ ይላል ጌታ እግዚአብሔር።



፸፬. ወለእመኒ አርዌ እኩየ ፈነውኩ ላዕሌሃ ለይእቲ ምድር፤ ወቀሠፍክዋ፤ ወአጠፍኣ ወኢይተርፍ፤ ዘያንሶሱ ቅድመ ውእቱ አርዌ።

፸፭.ወእመ ሀለዉ እሉ ፫ እደው ማዕከላ ሕያው አነ ይቤ አዶናይ እግዚአብሔር ከመ ኢያድኅኑ ደቂቆሙ ወአዋልዲሆሙ፤ ዘእንበለ ባሕቲቶሙ ዘይድኅኑ ወትጠፍእ ይእቲ ምድር[፷፫]። ወእመ ሀለዉ በዝ ዓለም ጻድቅ ወኃጥእ ኢይትኃጐል ጻድቅ ምስለ ኃጥእ እስመ ጽሑፍ ዘይብል ያዘንም ዝናመ ላዕለ ኄራን ወኃጥኣን ወእኩያን።

፸፮. ወእመሰቦ ዘይሔሊ ወይብል ኵነኔ ዕሩይ ላዕለ ኵሉ ኢኮነ ከመዝ፤ እስመ በውስተ ቀትልኒ ቦ ጽኑዕ ወቦ ዓዲ ዘይጸንዕ እምኔሁ።

፸፯.ወዘሰ ሞአ ይነሥእ ገሃደ አክሊለ መዊዖቱ እስመ ኢይኴንን እግዚአብሔር ጻድቀ ምስለ ኀጥእ ወኖኅኒ ኢተሰጥመ በማየአይኅ[፷፬] ወሎጥኒ ኢውዕየ በእሳት[፷፭]። ወረዓብኒ ዘማ ኢተኃጕለት[፷፮]።

፷፫. ኦገ ፲፬ . ፲፫. ፲፮
፷፬ ዘፍ. ፯ - ፳፪
፷፭. ዘፍ. ፲፱ . ፲፭.
፷፮.ኢያ ፮. ፳፪ ፳፫

፸፬. በዚያች አገር ላይ ክፉ አውሬን ብሰድ፤ ብቀሥፋትም፤ ባጠፋትም በዚያም አውሬ ፊት የሚያልፍ ባይተርፍ፤

፸፭. እነዚህ ሦስት ሰዎች በመካከልዋ ቢኖሩ እኔ ሕያው ነኝ እነርሱ ብቻቸውን ይድናሉ እንጂ ወንዶችና ሴቶች ልጆቻቸውን አያድኑም፤ ምድሪቱም ባድማ ትሆናለች ይላል ጌታ እግዚአብሔር፤ እንደ ተጻፈ ጻድቅና ኃጥእም በዚህ ዓለም ቢኖሩ ፤ ጻድቁ ከኃጥኡ ጋር አይጠፋም በደጋጎችና በኃጥአን ላይ በክፉዎችም ላይ እርሱ ዝናምን ያዘንማል›› የሚል ጽሑፍ አለና።

፸፮. ፍርድ በሁሉ ላይ ትክክል ነው የሚል ሰው ቢኖር ግን እንደዚህ አይደለም፤ በመግደል ስንኳ ጥኑ ነገር አለና፤ ዳግመኛም ከእርሱ የሚጸና አለና።

፸፯. ድል የነሣ ሰው የድል አድራጊነቱን አክሊል ይቀበላል፤ እግዚአብሔር ጻድቅን ከኃጥእ ጋራ አይቀጣምና፤ ኖኅም በማየ አይኅ ጊዜ አልሰጠመም፤ ሎጥም በገሞራ እሳት ጊዜ አልተቃጠለም፤ ረዓብ ዘማም በኢያሪኮ ጥፋት ጊዜ አልጠፋችም።

፸፰. ወእመሰ ትፈቅዱ ታእምሩ ዘኮነ በኀቤነ ይሁዳ አስቆሮታዊ እንዘ ኅቡር ምስሌነ ውስተ አሐዱ ቅኔ ተሀጒለ፤ ወሲሞን መሠርይ ዘነሥአ ማኅተመ እግዚአብሔር እስመ እሉ ፪ እኩያን እሙንቱ ወገሃደ ተዐውቀ እከዮሙ ይሁዳ ተሐንቀ[፺፯]:: ወሲሞን ሰረረ ላዕለ ወወድቀ ምድረ፤ ወኖኅ እንዘ ሀሎ ውስተ ታቦት ምስለ ደቂቁ፤ ካም በእከዩ አምጽአ መርገመ ላዕለ ወልዱ[፺፰]::

፸፱. ወበእንተዝ ለበውነ ከመ ኢይትፈደዩ አበው በኀጢአተ ውሉዶሙ፤ ወኢውሉድ በኃጢአተ አበዊሆሙ፤ ወዝንቱሰ ግብር እምቅድም ዕውቅ ውእቱ፤ ከመ ኢይትኴነና አንስት በአምታቲሆን፤ ወኢወራዙት በአንስትያሆሙ፤ ወአግብርት በአጋእዝቲሆሙ፤ ወአጋእዝት በአግብርቲሆሙ፤ ወኢአዝማድ በአዝማዲሆሙ ወኢአዕርክት በአዕርክቲሆሙ፤ ወኢኃጥኣን በጻድቃን፤ ወኢጻድቃን በኃጥኣን ፤ አላ ፩፩ ይትፈደይ በከመ ምግባሩ፤ እስመ ኖኅ ኢተፈድየ በኀጢአተ ሕዝብ፤ ወሎጥኒ ኢውዕየ በእሳተ ሰዶም፤ ወኢረዓብ በእንተ ኢያሪኮ፤ ኢደቂቀ እስራኤል በእንተ ግብጻውያን::

፸፰. በኛ ዘንድም የተደረገውን ልታውቁ ብትወዱ ግን የአስቆሮቱ ይሁዳ በአንድ አገልግሎት ከእኛ ጋራ አንድ ሲሆን ጠፋ፤ የእግዚአብሔርን ማኅተም የያዘ ሲሞን መሠርይም ጠፋ፤ እነ ዚህ ሁለቱ ክፉዎች ናቸውና፤ ክፋታቸውም ተገልጾ ታውቋልና፤ ይሁዳ ታነቀ፤ ሲሞንም ወደ ላይ ወጥቶ ወደ ምድር ወደቀ፤ ኖኅ ከልጆቹ ጋራ በመርከብ ውስጥ ሳለ ካም በክፋቱ በልጁ ላይ ርግማንን አመጣ::

፸፱. ስለዚህም አባቶች በልጆቻቸው ፤ ልጆችም በአባቶቻቸው ኀጢአት ፍዳን እንዳይቀበሉ አስ ተዋልን፤ ይህም ሥራ ከቀድሞ ጀምሮ የታወቀ ነው፤ ሴቶች በባሎቻቸው እንዳይቀጡ፤ ወንዶችም በሚስቶቻቸው፤ ባሮችም በጌቶቻቸው፤ ጌቶችም በባሮቻቸው፤ ዘመዶችም በዘመዶቻቸው፤ ወዳጆችም በወዳጆቻቸው፤ ኃጥአንም በጻድቃን እንዳይቀጡ፤ ጻድቃንም በኃጥአን እንዳይቀጡ፤ የታወቀ ነው፤ ነገር ግን እያንዳንዱ እንደሥራው ፍዳውን ይቀበላል፤ ኖኅ በሕዝቡ ኃጢአት ፍዳን አልተቀበለምና፤ ሎጥም በሰዶም እሳት አልተቃጠለምና፤ ረዓብም በኢያሪኮ ነገር አልጠፋችምና፤ እስራኤልም በግብጻውያን ነገር አልጠፉምና::

፺፯ ግብ፡ ሐዋ ፩. ፲፰
፺፰ ዘፍ. ፱ : ፳፭



፹.ኢመፍትውኬ ለነ ንትሉ አሠሮሙ ወምግባሮሙ ለከሓድያን፤ ወዐማፅያን፤ ወቀታልያን ወእለ ያመክንዩ ለእከይ፤ ወጸላእያን እለ ድልዋን ለመዊት፤ እስመ ኵሉ በከመ ምግባሩ ይትፈደይ በከመ ይቤ ዳዊት እስመ አንተ ትፈድዮ ለኵሉ በከመ ምግባሩ[፺፱]:: ወበእንተዝ ንርድኦሙ ለምንዱባን ርቱዕ፤ ወነሐውጾሙ ለሕሙማን፤ ወንሚጠሙ ለኃጥኣን እለ ቄስሉ በግብረ ኀጢአት፤ ንምሀሮሙ ወናለብዎሙ በቃለ ተግሣጽ ከመ ይድኀኑ እሞተ ኀጢአት::

፹፩. እስመ አኮ ጥዑያን ዘይፈቅድዎ ለዐቃቤ ሥራይ አላ ሕሙማን፤ እስመ ኢይፈቅድ አቡነ ዘበሰማያት ይትሀጐል አሐዱ እምእሉ ንኡሳን::

፹፪. ወይእዜኒ ኦ አኀውየ ኢንስማዕ ቃሎሙ ለአብዳን፤ ወጽሉላነ ልብ፤ አላ ንፈጽም ሥምረቶ ለእግዚአብሔር አኃዜ ኵሉ በእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ዘሎቱ ስብሐት ለዓለመ ዓለም አሜን::

፺፱. መዝ. ፷፩. ፲፪

፹. ለእኛም የከሃዲዎችንና የዐመፀኞችን የገዳዮችንና ለክፋት የሚያመካኙትን፤ ለሞት የሚገቡ የጠላቶችን ፍለጋቸውንና ግብራቸውን ልንከተል አይገባም፤ ዳዊት «አንተ ለሁሉ እንደ ሥራው ትከፍለዋለህ» እንዳለ፤ ሁሉም እንደ ሥራው ፍዳውን ይቀበላልና፤ ስለዚህም ነገር የተቸገሩትን ልንረዳቸው፤ የታመሙትንም እንጠይቃቸው ዘንድ፤ በኀጢአት ሥራ የቈሰሉ ኃጥአንንም ራርተን እን መልሳቸው ዘንድ፤ በምክር ቃልም ከኀጢአት ሞትም ይድኑ ዘንድ አእምሮ ልናሳድርባቸው ይገባል::

፹፩. ባለመድኀኒትን የሚሹት የታመሙት ናቸው እንጂ፤ ጤነኞች አይደሉምና፤ ሰማያዊ አባታችን ከእነዚህ ከታናናሾቹ አንዱ ይጠፋ ዘንድ አይወድምና::

፹፪. ዛሬም ወንድሞቼ ሆይ ልባቸው የተሸፈነ የሰነፎችን ቃል አንስማ፤ ነገር ግን ለዘለዓለሙ ምስጋና ሲገባው በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ሁሉን የያዘ የእግዚአብሔር አብን ፈቃድ እን ፈጽም፤ ለዘለዓለሙ አሜን ::

## አንቀጽ ፳

ከመ ኢመፍትው ለኤጲስ ቆጶስ ይስማዕ ነገረ ውዴት::

፩. ወኢትስማዕ ነገረ ውዴት በኀበ ብእሲ እኩይ ዘይነብብ ሐሰተ ላዕለ ካልዑ አላ አንተሰ ረሲ ትውክልተ በኀበ እግዚአብሔር ወሥርየሙ ለሕዝብከ በከመ ይደሉ ::

፪. ወኢይትዐበይ ወልድ ላዕለ አቡሁ፤ወኢገብር ላዕለ እግዚኡ፣ ወኢረድእ ላዕለ መምህሩ፣ ወኢ ወዓሊ ላዕለ ነጋሢ፣ ወኢ ሕዝባዊ ላዕለ ኤጲስ ቆጶስ፣ እስመ ኢመፍትው ይሳተፍ መምህር ምስለ ዐላውያን ወዐማፅያን፤ እስመ ኢይፈቅድ ኃጥእ ቃለ ተግሣጽ::

፫. ይቤ ሕዝቅኤል ነቢይ ወነበበኒ እግዚአብሔር ወይቤለኒ: ወልደ እጓለ እመሕያው ምንት በኀቤክሙ ዝንቱ ምሳሌ ዘይብሉ ደቂቀ እስራኤል አበው በልዑ ቆዐ፤ ወደቂቅ ፀርሱ ስነኒሆሙ[፩]::

፬. ሕያው አነ ይቤ እግዚአብሔር አዶናይ ከመ ኢይብልዋ ዳግመ ለዛቲ ምሳሌ በውስተ እስራኤል::

፩.ሕዝ.፲፰.፪ .

## አምስተኛ አንቀጽ

ኤጲስ ቆጶሱ የነገር ሥራን መስማት እንደማይገባው ይናገራል፤

፩. በባልንጀራው ላይ ሐሰትን ከሚናገር ከክፉ ሰው ዘንድ የነገር ሥራን አትስማ፤ነገር ግን አንተ እምነትህን በእግዚአብሔር አድርግ፤ ወገኖችህንም በሚገባ አዘጋጃቸው።

፪. ልጅ በአባቱ ላይ አይታበይ፤ ባሪያም በጌታው ላይ፣ ደቀ መዝሙርም በመምህሩ ላይ፣ ሎሌም በንጉሡ ላይ፣ ሕዝባዊም በኤጲስ ቆጶሱ ላይ አይታበይ፤ መምህር ከከሓዲዎችና ከዐመፀኞች ጋር አንድ ይሆን ዘንድ አይገባምና፣ ኃጥእም ሰው የተግሣፅ ቃልን አይወድምና::

፫.ነቢዩ ሕዝቅኤል እንዲህ አለ፣ የእግዚአብሔርም ቃል ወደ እኔ እንዲህ ሲል መጣ፤ በእስራኤል ልጆች አባቶች ጨርቋ የወይን ፍሬ በሉ፤ የልጆችም ጥርሶች ጠረሱ ብላችሁ በመካከላችሁ የምትመስሉት ምሳሌ ምንድን ነው?

፬.እኔ ሕያው ነኝ፣ እንግዲህ ወዲህ ይህን ምሳሌ በእስራኤል ዘንድ አትመስሉትም ይላል ጌታ እግዚአብሔር፤



፭.እስመ ነፍስ ኵሉ ዚአየ ውእቱ ከመ ነፍሰ አብ፣ ከማሁ ነፍሰ ወልድ ዚአየ ውእቱ ነፍስ እንተ አበሰት ይእቲ ትመውት::

፮. ወብእሲሰ ጻድቅ ዘይገብር ጽድቀ ወርትዐ::

፯.ወኢበልዐ በውስተ አድባር ወኢያንሥአ አዕይንቲሁ ኀበ ሕሊናሆሙ ለቤተ እስራኤል ወኢያርኵሰ ብእሲተ ቢጹ ወኢቀርበ ብእሲተ ትክት::

፰.ወኢዐመፀ ቢጾ ፣ ወአግብአ አኀዘ ዕዳሁ፣ ወኢሄደ፣ ወኢተዐገለ ወወሀበ እምእክሉ ለነዳይ ወአልበሰ እምልብሱ ለዕሩቅ::

፱.ወኢለቅሐ ወርቆ በርዴ፤ወኢነሥአ ዘዐመፃ፣ ወሜጠ እዴሁ እምኀጢአት፤ ወገብረ ፍትሐ ወጽድቀ ማዕከለ ብእሲ ወቢጹ::

፲. ወሖረ በትእዛዝየ፣ ወዐቀበ ሕግየ ወገብረ ጽድቀ ጻድቅ ውእቱ ወሐይወተ የሐዩ ይቤ አዶናይ እግዚአብሔር ::

፲፩. ወለእመ ወለደ ወልደ ኃጥአ ወቀታሌ ነፍስ ዘይገብር ዐመፃ::

፭. እነሆ ነፍሳት ሁሉ የኔ ናቸው፤ የአባት ነፍስ የኔ እንደ ሆነች፣ እንዲሁ የልጅ ነፍስ የኔ ናት፤ ኀጢአት የምትሠራ ነፍስ እርስዋ ትሞታለች ፡

፮. ሰውም ጻድቅ ቢሆን ፍርድ ንና ቅን ነገርንም ቢያደርግ ::

፯. በተራራ ላይም ባይበላ፣ ዐይኖቹንም ወደ እስራኤል ቤት ጣዖታት ባያነሣ፣ የባልንጀራውንም ሚስት ባያረክስ፣ አደፍም ወዳለባት ሴት ባይቀርብ፡፡

፰. ሰውንም ባያስጨንቅ፣ ለባለዕዳም መያዣውን ቢመልስ፣ ፈጽሞም ባይቀማ፣ ከእንጀራውም ለተራበ ቢሰጥ የተራቆተውንም ከልብሱ ቢያለብስ::

፱. ገንዘቡን በአራጣ ባያበድር፣ አትርፎም ባይወስድ፣ እጁንም ከኀጢአት ቢመልስ፣ በሰውና በሰው መካከልም የእውነትን ፍርድ ቢፈርድ::

፲.በትእዛዜም ቢሄድ፣ እውነትንም ለማድረግ ፍርዴን ቢጠብቅ፣ እርሱ ጻድቅ ነው፤ ፈጽሞም በሕይወት ይኖራል ይላል ጌታ እግዚአብሔር::

፲፩. እርሱም ቀማኛና ደም አፍሳሽ ልጅን ከዚህ ሁሉ አንዳቸውን የሚያደርገውን ቢወልድ::

፲፪. ወኢሖረ በፍኖተ አቡሁ ጻድቅ፣ ወበልዐ በውስተ አድባር ወአርኰሰ ብእሲተ ቢጹ::

፲፫. ወተዐገለ ነዳየ ወምስኪነ ወሄደ፣ ወዐመፀ፣ ወኢያግብአ አኀዘ ዕዳሁ፣ ወሜጠ አዕይንቲሁ መንገለ ጣዖት፣ ወገብረ ዐመፃ::

፲፬. ወለቅሐ በርዴ ወአስተናድአ ወነሥአ ዘሰርቅ ዘከመዝ ኢየሐዩ ሕይወተ፤ በኵሉ ዝንቱ ኀጢአቱ ዘገብረ ሞተ ይመውት ወይገብእ ደሙ ላዕሌሁ::

፲፭. ወለእመ ወለደ ወልደ ወርእየ ኵሎ ኀጢአተ አቡሁ ዘገብረ ወፈርሀ፣ ወኢገብረ ከማሁ::

፲፮. ወኢበልዐ ውስተ አድባር፣ ወኢያንሥአ አዕይንቲሁ መንገለ ሕሊናሆሙ ለቤተ እስራኤል፣ ወኢያርኰሰ ብእሲተ ቢጹ::

፲፯. ወኢተዐገለ ሰብአ፣ ወአግብአ አኀዘ ዕዳሁ፣ ወኢያስተናድአ፤ ወኢሄደ፤ ወአብልዐ እምእክሉ ለርኁብ ወአልበሰ እምልብሱ ለዕሩቅ::

፲፪. እርሱም በጻድቅ አባቱ መንገድ ባይሔድ፣ በተራራም ላይ ቢበላ፣ የባልንጀራውንም ሚስት ቢያረክስ::

፲፫. ድሀውንና ችግረኛውን ቢያስጨንቅ፣ ቢቀማም መያዣውንም ባይመልስ፣ ዐይኖቹንም ወደ ጣዖት ቢያነሣ፣ ርኩስንም ነገር ቢያደርግ ::

፲፬. በአራጣ ቢያበድር አትርፎም ቢወስድ፣ እንዲህ ያለ ሰው በሕይወት አይኖርም ፤ ይህን ርኩሰት ሁሉ አድርጓልና ፈጽሞ ይሞታል፤ ደሙም በላዩ ይመለሳል::

፲፭.እነሆም ልጅን ቢወልድ እርሱም አባቱ የሠራውን ኀጢአት አይቶ ቢፈራ፣ እንደርሱም ባይሠራ::

፲፮. በተራራ ላይ ባይበላ፣ ዐይኖቹንም ወደ እስራኤል ቤት ጣዖታት ባያነሣ፣ የባልንጀራውንም ሚስት ባያረክስ::

፲፯. ሰውንም ባያስጨንቅ፣ መያዣውንም ባይወስድ፣ ባይቀማም፣ ከእንጀራውም ለተራበ ቢሰጥ፣ ለተራቈተውም ልብስን ቢያለብስ::



፲፰. ወሜጠ እዴሁ እምዐመፃ ወኢነሥአ ርዴ ወንዋየ ዐመፃ፤ ወገብረ ጽድቀ፤ወሖረ በትእዛዝየ ኢይመውት በኀጢአተ አቡሁ፤ አላ ሐዩወ የሐዩ::

፲፱. ወአቡሁሰ ለእመ ገፍዐ፣ ወዐመፀ፣ ወሄደ ወተዐገለ፣ ወገብረ ዘኢይከውን በማዕከለ ሕዝቡ ይመውት በጌጋዩ::

፳. ወትብሉ በእፎ ኢይትፌደይ ወልድ በኀጢአተ አቡሁ፣ እስመ ገብረ ወልድ ጽድቀ ወምጽዋተ፣ ወዐቀበ ኵሎ ሕግየ ወገብረ ሕይወተ የሐዩ::

፳፩. ወነፍስ እንተ አበሰት ትመውት ሞተ ወወልድ ኢይትፌደይ በኀጢአተ አቡሁ፤ ወአብ በኀጢአተ ወልድ ኢይትፌደይ ጽድቁ ለጻድቅ ለርእሱ ወኀጢአቱ ለኃጥእ ላዕሌሁ፣

፳፪. ወለእመ ተመይጠ ኀጥእ እምኵሉ ኀጢአቱ ዘገብረ ወዐቀበ ኵሎ ትእዛዝየ፤ ወገብረ ጽድቀ ወምጽዋተ፣ ሕይወተ የሐዩ፤ ወኢይመውት::

፲፰. እጁንም ከዐመጽ ቢመልስ፣ አራጣንም አትርፎ ባይወስድ፣ ፍርዴንም ቢያደርግ፣ በትእዛዜም ቢሄድ እርሱ ፈጽሞ በሕይወት ይኖራል እንጂ በአባቱ ኀጢአት አይሞትም::

፲፱. አባቱ ግን ፈጽሞ በድሎአልና፣ ወንድሙንም ቀምቷልና፣ በሕዝቡም መካከል ክፉን ነገር አድርጓልና እነሆ እርሱ በበደሉ ይሞታል::

፳. እናንተ ግን ልጅ የአባቱን ኀጢአት ስለምን አይሸከምም ትላላችሁ፣ ልጅ ፍርድንና ቅን ነገርን በአደረገ ትእዛዜንም ሁሉ በጠበቀና በአደረገ ጊዜ ፈጽሞ በሕይወት ይኖራል::

፳፩. ኀጢአትን የምትሠራ ነፍስ እርሷ ሞትን ትሞታለች፤ ልጅ የአባቱን ኀጢአት አይሸከምም፤ አባትም የልጁን ኀጢአት አይሸከምም፤ የጻድቅ ጽድቁ በራሱ ላይ ይሆናል፤የኃጢአተኛውም ኃጢአት በራሱ ላይ ይሆናል::

፳፪. ኀጢአተኛውም ከአደረጋት ኀጢአት ሁሉ ቢመለስ፣ ትእዛዜንም ሁሉ ቢጠብቅ፣ ፍርዴንና ቅን ነገርንም ቢያደርግ፤ ፈጽሞ በሕይወት ይኖራል እንጂ አይሞትም::

፳፫. ወኵሉ ኀጢአቶ ዘገብረ ኢይዜከር ሎቱ፤ ዳዕሙ በጽድቁ ዘገብረ የሐዩ ቦቱ ::

፳፬. ቦኑ ፈቂደ እፈቅድ ከመ ይሙት ኃጥእ ይቤ አዶናይ እግዚአብሔር፤ ዳእሙ ከመ ይት መየጥ እምፍኖቱ እኩይ ወይሕየው::

፳፭. ወለእመ ተመይጠ ጻድቅ እምጽድቁ፣ ወገብረ ኀጢአተ ይመውት በኵሉ ጌጋዩ ዘገብረ ውእቱ ኃጥእ ኵሎ ጽድቆ ዘገብረ ኢይዜከር ሎቱ፤ ወበአበሳሁ ዘአበሰ ቦቱ ይመውት፤

፳፮. ወትብሉ ኢኮነ ርቱዐ ፍኖተ እግዚአብሔር፣ ስምዑኬ ቤተ እስ ራኤል፣ ፍኖትየኑ ኢኮነ ርቱዐ አኮኑ ፍኖትክሙ ኢኮነ ርቱዐ፤

፳፯. እምከመ ተመይጠ ጻድቅ እምጽድቁ ወገብረ ኀጢአተ ይመ ውት በጌጋዩ ዘገብረ ቦቱ::

፳፰. ወእመ ተመይጠ ኃጥእ እም ኀጢአቱ ዘገብረ ወገብረ ጽድቀ ወርትዐ ዘከመዝ ነፍስ የሐዩ::

፳፫. የበደለው በደል ሁሉ አይታ ሰብበትም፤ በሠራው ጽድቅ በሕ ይወት ይኖራል እንጂ::

፳፬. «በውኑ ኀጢአተኛ ይሞት ዘንድ መፍቀድን እፈቅዳለሁን?» ይላል ጌታ እግዚአብሔር፣ ከክፉ መንገዱ ይመለስና በሕይወት ይኖር ዘንድ ነው እንጂ::

፳፭. ጻድቁ ግን ከጽድቁ ቢመ ለስ፣ኀጢአትንም ቢሠራ፣ ኃጢ አተኛውም እንደሚያደርገው ርኵሰት ሁሉ ቢያደርግ በሕይ ወት ይኖራልን? የሠራው ጽድቅ ሁሉ አይታሰብለትም፤ በአደረ ገው ዐመፅና በሠራት ኀጢአት በዚያች ይሞታል፤

፳፮. እናንተ ግን የጌታ መንገድ የቀናች አይደለችም ትላላችሁ፤ የእስራኤል ቤት ሆይ! እንግዲህ ስሙ፤ በውኑ መንግዴ የቀናች አይደለችምን፤ ይልቅስ የእናንተ መንገድ ያልቀናች አይደለችምን::

፳፯. ጻድቁ ከጽድቁ ቢመለስ ኀጢ አትንም ቢሠራ፣ እርሱ በአደረ ገው በደል ይሞታል::

፳፰. ኀጢአተኛውም ከሠራው ኀጢአት ቢመለስ፣ ፍርድንና ቅን ነገርንም ቢያደርግ ነፍሱን ይጠብቃል::



፳፱. ወርእየ ወተመይጠ እምኵሉ ኀጢአቱ ዘገብረ ሕይወተ የሐዩ ወኢይመውት::

፴. ወይብሉ ቤተ እስራኤል ኢኮነ ርቱዐ ፍኖተ እግዚአብሔር ቦኑ ፍኖትየ ኢኮነ ርቱዐ ቤተ እስራ ኤል፣ አኮኑ ፍኖትክሙ ኢኮነ ርቱዐ::

፴፩. በበይነ ዝንቱ ለኵልክሙ በከመ ፍኖትክሙ እኴንነክሙ ቤተ እስራኤል ይቤ አዶናይ እግዚአ ብሔር፣ ተመየጡ ወነስሑ እም ኀጢአትክሙ ወኢይመጽአክሙ መቅሠፍተ ኀጢአትክሙ[፪]::

፴፪. ወግድፉ እምላዕሌክሙ ኵሎ ጌጋየክሙ ዘአበስክሙ ሊተ፣ ወግበሩ ለክሙ ልበ ሐዲሰ ወመ ንፈሰ ሐዲሰ ወለምንት ትመ ውቱ በኃጢአትክሙ ቤተ እስራ ኤል::

፴፫. እስመ ኢይፈቅድ ለክሙ ሞተ ትሙቱ ይቤ አዶናይ እግዚአብሔር፤ ዘእንበለ ከመ ትነስሑ ወትሕየዉ::

፪.ሕዝ. ፲፰. ፴፩. ፴፪.

፳፱. ከሠራው ሁሉ በደል አይቶ ተመልሷልና ፈጽሞ በሕይወት ይኖራል እንጂ አይሞትም::

፴. ነገር ግን የእስራኤል ቤት የጌታ መንገድ የቀናች አይደለችም ይላሉ፤ የእስራኤል ቤት ሆይ! በውኑ መንገዴ የቀናች አይደለ ችምን ይልቅስ የናንተ መንገድ ያልቀናች አይደለችምን::

፴፩. የእስራኤል ቤት ሆይ! ስለ ዚህ እንደ መንገዱ በየሰዉ ሁሉ እፈርድባችኋለሁ ይላል ጌታ እግ ዚአብሔር፤ ንስሐ ግቡ፤ ኀጢአ ትም ዕንቅፋት እንዳይሆንባችሁ ከኀጢአታችሁ ሁሉ ተመለሱ::

፴፪. የበደላችሁትን በደል ሁሉ ከእናንተ ጣሉ፣ አዲስ ልብና፣ አዲስ መንፈስም ለእናንተ አድ ርጉ፤ የእስራኤል ቤት ሆይ! በኃ ጢአታችሁ ስለምን ትሞታላ ችሁ?

፴፫. ሞትን ትሞቱ ዘንድ አልፈ ቅድምና ይላል ጌታ እግዚአብ ሔር፣ ስለዚህ በንስሐ ተመለ ሱና በሕይወት ኑሩ ::

## አንቀጽ ፮

ኤጲስ ቆጾሳት ይትወከፉ ንስሓ
ሆሙ ለእለ ይትመየጡ በፍቅር
ወበየውሃት ።

፩. ኦ ፍቁራን አኃውየ ርእዩ ብዝኀ
ምሕረቱ ለእግዚአብሔር አምላክነ
ኄር፣ወጻድቅ፣ ወመፍቀሬ ሰብእ፣
ወመስተሣህል ለእለ ይትመየጡ
ውስተ ንስሓ፤ እስመ ኢይፈቅድ
እለ ይፈትሑ በአክብዶ፣ ወበጽል
ሑተ ልብ ዘእንበለ ምሕረት፤ አላ
ባሕቱ ይሚጥዎሙ ወይትወከ
ፍዎሙ ለእለ አበሱ በሠናይ አም
ልኮ ከመ ይክህሉ ገቢአ ውስተ
ንስሓ።
፪. ወእመሰ ኢመሐሩ ኤጲስ ቆጾ
ሳት ወኢገብሩ ከመዝ ይትኀሠሥ
እግዚአብሔር እምኔሆሙ ኀጢ
አተ ሕዝቡ፤ በከመ ይቤ ኢሳይ
ያስ ገሥጽዎሙ ለሕዝብየ ይቤ
እግዚአብሔር፣ ካህናት ንንብዋ
ለኢየሩሳሌም ዘይበውእ ውስተ
ልባ፣ መፍትው ለኤጲስ ቆጾሳት
ይሕትትዎሙ ሕዝብየ፤ ወእመሰቦ
ዘአበሱ ይሚጥዎሙ ውስተ
ንስሓ፣ ከመ ይርከቡ ለርእሶሙ
ዐስበ ሠናየ፤ ወእመሰቦ ዘኢመ
ሐሩ ወኢሜጥዎሙ ለሕዝብ
ውስተ አምልኮ ሠናይ ይረክቡ
ኵነኔ ።

## ስድስተኛ አንቀጽ

ኤጲስ ቆጾሳት በፍቅርና፣ በቅን
ነት የሚመለሱትን ንስሐቸውን
ይቀበሉ፤

፩. የተወደዳችሁ ወንድሞቼ ሆይ!
ወደ ንስሓ ለሚመለሱ ሰዎች
ቸር፣ ጻድቅ፣ ሰው ወዳጅና
ይቅር ባይ የሚሆን የፈጣሪያች
ንን የእግዚአብሔርን የቸርነቱን
ብዛት እዩ፤ ያለምሕረት በማክበ
ድና በልብ ተንኰል የሚፈርዱ
ትን አይወድምና ነገር ግን ወደ
ንስሓ መመለስን ይችሉ ዘንድ
የበደሉትን በበጎ አምልኮ
መልሰው ይቀበሉአቸው ።
፪. ኤጲስ ቆጾሳት ግን ባይራሩ፣
እንደዚህም ባያደርጉ እግዚአብ
ሔር የሕዝቡን ኀጢአት ከእነ
ርሱ ይፈልጋል፤‹‹ኢሳይያስ ወገ
ኖቼን ምከሯቸው፤ ኢየሩሳሌም
ንም ወደ ልቧ የሚገባ ነገርን
ንገሯት›› አለ እግዚአብሔር እን
ዳለ፣ ለኤጲስ ቆጾሳት ወገኖችን
ይመረምሯቸው ዘንድ ይገባ
ቸዋል፤ የበደሉም ቢኖሩ በጎ
ዋጋን ለራሳቸው ያገኙ ዘንድ
ወደ ንስሐ ይመልሷቸው፤ ሕዝ
ቡንም ወደ በጎ አምልኮት አስተ
ምረው ያልመለሷቸው ቢኖሩ
ግን ቅጣትን ያገኛሉ ።



፫. ወይእዜኒ ንትወከፍ ንስሓ
ሆሙ በፍሥሓ ወበፍቅር ለእለ
ተመይጡ ኀበ እግዚአብሔር፤ወለ
እለሂ አበሱ ንፍታሕ ሳዕሌሆሙ
በሣህል ወበምሕረት በከመ ይደሉ
ለንስሓ።
፬. ወእመሰ ርኢከ ብእሴ ዘይገብር
ኀጢአተ ወይድኀፅ ውስተ ስሕ
ተት እንሥኦ እምድቀቱ፤ወእመሰ
አስተጠዐምከ ሎቱ ምግባሮ ናሁ
ቀተልኮ ለእኍከ፤ ወባሕቱ ርቱ
ዕሰ ታንሥኦ ለዘድኀፀ እምድቀቱ
ከመ ኢይማስን፤ ወርእዮሙ ካል
አን ይትሜሀሩ ወይለብዉ ወይት
ወከፉ ቃለ ተግሣጽ።

፭. ኢርቱዕ ለኤጲስ ቆጶስ ይትጐ
ናደይ በእንተ ኀጢአተ ሕዝብ
ወዓዲ ኢይትሀከይ ጸሐቆሙ ለእለ
የኀሥሡ ንስሓ ከመ ኢይ
ትሀጐል መርዔቱ ለእግዚአብሔር
በሀኬተ ዚአሁ፤ እስመ በእንቲ
አሆሙ ነበበ እግዚአብሔር በአፈ
ኤርምያስ ነቢይ እንዘ ይብል
ኖሎት ብዙኃን አማሰኑ ዐፀደ
ወይንየ ወአርኰሱ መክፈልትየ፤
ወረሰይዋ ለመክፈልትየ፤ እንተ
አፈቅር በድወ ወዐፀ፤ ወኮነት
ለሙስና ወለኀጕል፤ ወበእንቲ
አየ ኀልቀት ኵላ ምድር ወማሰ
ነት[፩]። :

፩. ኤር ፲፪ ፡ ፲ ፡ ፲፩

፫. አሁንም ወደ እግዚአብሔር
የተመለሱትን በደስታና በፍቅር
ንስሓቸውን እንቀበል፤ የበደሉት
ንም ለንስሓ እንደሚገባ በፍቅርና
በምሕረት እንፍረድላቸው ።

፬. ኀጢአትን የሚሠራ በስሕ
ተትም የሚሰነካከል ሰው ብታይ
ከወደቀበት አንሣው፤ ሥራውን
ብታጣጥምለት ግን እነሆ ወንድ
ምህን ገደልኸው፤ ነገር ግን
የተሰነካከለውን ከመውደቁ የተ
ነሣ እንዳይጐዳ ታነሣው ዘንድ
ይገባል፤ሌሎችም አይተው ይማ
ራሉና ያስተውላሉም፤ የምክር
ንም ቃል ይቀበላሉ ።
፭. ስለ ሕዝቡ ኀጢአት ይዘገይ
ዘንድ ለኤጲስ ቆጶስ አይገባ
ውም፤ ዳግመኛም በሱ ስንፍና
የእግዚአብሔር መንጋዎች እንዳ
ይጐዱ ንስሐ የሚፈልጉትን ትጋ
ታቸውን ቸል አይበል፣ እግ
ዚአብሔር ስለእነርሱ በነቢዩ በኤ
ርምያስ ቃል እንዲህ ብሎ
ተናግሯልና›› ምእመናንን የሚ
ጠብቁ ብዙዎች መምህራን ወይን
ሕጌን አጠፉ፤ የምወዳት እድል
ፋንታዬን ጽዋ ተርታዬንም
ምድረ በዳ አደረጓት፤ ለጥፋትም
ሆነች፤ስለኔም ምድር ሁላ ፈጽማ
ጠፋች›› ብሎ ተናግሯልና።

፮. ወአንተኒ እመ ርኢከ ዘይኤብስ አዝዝ ዲያቆናተ ያውጽእዎ ወይስድድዎ አፍኣ ወይገሥጽዎ ወይምህርዎ ከመ ርእዮሙ ካልአን ይፍርሁ፤ ወእምከመ ተመይጠ ወገብአ ውስተ ንስሓ ይስአሉ፤ ወያስተብቍዑ ኀበ እግዚአብሔር ወኀበ ኤጲስ ቆጶስ ከመ ይምህሮ፤ እስመ መድኀን ስአለ ኀበ አቡሁ በከመ ጽሑፍ ውስተ ወንጌል በእንተ ኃጥአን «አባ ሥረይ ሎሙ እስመ በዘኢየአምሩ ይገብሩ[፬]»።

፯. ወእምዝ ይሕትትዎ ለዘአበሰ ከመ ይኅድግ ፍኖቶ እኪተ፤ ወእምከመ ተአመነ ኀጣውዖ ወተመይጠ ውስተ ንስሓ ያብሕዎ ይባዕ ውስተ ቤተ ክርስቲያን፤ ወየአዝዝዎ ይጹም መጠነ ገብረ ኀጢአተ ፪ተ ሰባዔ፤ አው ፫ተ፤ አው ፭ተ፤ አው ፯ተ ሰባዔ።

፰. ርቱዕ ለኃጥእ ትምህሮ፤ ወታለብዎ፤ ወትገሥጾ ዘእንበለ መዓት ወአድልዎ ከመ ያትሕት ርእሶ ፤

፬ ሉቃ ፳፫ ፡ ፴፬

፮. አንተም የሚበድል ሰውን ብታይ ሌሎች አይተው እንዲፈሩ ከቤተ ክርስቲያን ውጭ አስወጥተው ወስደው ይመክሩትና ያስተምሩት ዘንድ ዲያቆናትን እዘዛቸው፤ ወደ ንስሓ ቢመለስ ግን ወደ እግዚአብሔር ይለምኑ፤ ይማልዱም፤ ይቅር ይለውም ዘንድ ወደ ኤጲስ ቆጶሱ ይለምኑ፤ «አባት ሆይ! የማያውቁትን ያደርጋሉና ይቅር በላቸው» ተብሎ በወንጌል እንደ ተጻፈ መድኃኒታችን ወደ አባቱ ለምኗልና።

፯. ከዚህ በኋላ ክፉ ሥራውን ይተው ዘንድ የበደለውን ይመርምሩት፤ ኀጢአቱን አምኖ ወደ ንስሓ ቢመለስ ግን ወደ ቤተ ክርስቲያን ይገባ ዘንድ ይፍቀዱለት፤ ኀጢአትንም ስለ ሠራ ሁለት ሱባዔ፤ ወይም ሦስት ሱባዔ፤ ወይም አምስት ሱባዔ፤ ወይም ሰባት ሱባዔ፤ ይጾም ዘንድ ይዘዙት።

፰. በፊቱ በቆመ ጊዜ ይቅርታንና ምሕረትን እንዲያገኝ ራሱን ዝቅ አድርጎ ወደ እግዚአብሔር ይለምን ዘንድ ኃጢአተኛውን



ወይስአል ኀበ እግዚአብሔር ከመ ይርከብ ሣህለ ወምሕረተ እመ ይቀውም ቅድሜሁ፤ እስመ ይቤ እመሰ ኀጢአተነ ትትዐቀብ እግዚኦ እግዚኦ መኑ ይቀውም ቅድሜከ፤ እስመ እምኀቤከ ውእቱ ሣህል፤ወምሕረት ውስተ እዴከ[፭]፤ ግበር እንከ ከመዝ ወአበይን እስመ ይቤሎ ለቃየን አበስከ አርምም፤[፮] እንከ ወኢታንሥእ እዴከ።

፱. ወባሕቱ ርቱዕሰ ለኀጥእ ይኅዝን ወይተክዝ ወይመንን ርእሶ፤ ንለቡ ቃሎ ዘይቤ እግዚአብሔር ለሙሴ በእንተ ማርያም፤ ሶበ አቡሃ ተፍአ ትፍአቶ ውስተ ገጻ እምኢኀፍረትኑ ሰቡዐ መዋዕለ፤ ወትትገሐሥ አፍአ እምትዕይንት ሰቡዐ መዋዕለ፤ ወእምዝ ትበውእ።

፲. ወተግሕሠት ማርያም አፍአ እምትዕይንት ሰቡዐ መዋዕለ፤ወኢግዕዙ ሕዝብ እስከ ነጽሐት ማርያም፤ወእምድኅረዝ ግዕዙ ሕዝብ[፯]።

፭ መዝ ፻፳፱ ፡ ፫
፮ ዘፍ ፬ ፡ ፯
፯ ዘኁል ፲፪ ፡ ፲፬ - ፲፭

ያለቁጣና ያለ አድልዎ ታስተምረው፤ ታሳውቀውና ትመክረው ዘንድ ይገባል፤ ኀጢአትን የምትጠባበቅ ከሆነ አቤቱ! አቤቱ! በፊትህ ማን ይቆማል? ብሏልና፤ ይቅርታ ካንተ ዘንድ ነውና፤ ምሕረትም በእጅህ ነውና፤ እንግዲህ እንደዚህ አድርገህ ፍረድ፤ እግዚአብሔር ቃየንን «በድለሃልና ዝም በል እጅህን ወደ ሰማይ አታንሣ» ብሎታልና።

፱. ነገር ግን ለኀጢአተኛ ሰው ያዝንና ይተክዝ ራሱንም ይንቅ ዘንድ ይገባዋል፤ እግዚአብሔር ስለ ማርያም ለሙሴ የተናገረውን ቃሉን እናስተውል፤ አባቷ ምራቁን በፊቷ ቢተፋባት እንኳ ሰባት ቀን ባላፈረችም ነበርን፤ አሁንም ሰባት ቀን ከሠፈር ውጭ ተዘግታ ትቀመጥ፤ ከዚያም በኋላ ወደ ሰፈር ትመለስ።

፲. ማርያምም ከሰፈር ውጭ ሰባት ቀን ተለይታ ተቀመጠች፤ እስክትነጻም ድረስ ሕዝቡ አልተጓዙም፤ ከዚያም በኋላ ሕዝቡ ተጓዙ።

፲፩. ንግበር እንከ ከመዝ ለእለ ይፈቅዱ ንስሓ እምኀጣውኢሆሙ ንሥራዕ ሎሙ ዕድሜ ዓመታት መጠነ አበሱ በዘይኔስሑ፤ ወአመ ነስሑ ንትወከፎሙ በከመ ይም ሕሩ አበው ውሉዶሙ፡፡

፲፪. ወእመሰ ኤጲስ ቆጶሳት ወባ ዕዳንሂ ሥዩማን ቦሙ ስዕበት ወነውር፤ወኢይፈትሑ ርትዐ ለዕ ጓለ ማውታ፣ ወለነዳይ፣ ወለመ ዓስብ፣ አላ ይፈትሑ በአድልዎ ከመ ይንሥኡ ርጼ ወሕልያነ፤ እሉኬ ይትሀጕሉ ምስለ መደል ዋን በከመ ጽሑፍ ውስተ ወን ጌል ዘይቤ ለምንት ትኔጽር ኀሠረ ውስተ ዐይነ ቢጽከ ወኢት ሬኢ ሠርዌ ዘውስተ ዐይንከ[፮]፡፡

፲፫.ወይትዐቀቡ እንከ ኤጲስ ቆጶ ሳት ወካህናት ከመ ኢይትረከብ በላ ዕሌሆሙ ዘከመዝ ግብር ከመ ኢይትዐቀፉ ካልአን ርእዮሙ ዘንተ እኩየ ምግባረ እስመ እኩያን የኀሥሡ ምክንያተ ከመ ያማስኑ

፮ ማቴ ፯ ፡ ፫

፲፩.እንግዲህ ከኀጢአታቸው ተለ ይተው ንስሓን ለሚሹ ሰዎች እንዲህ እናድርግ፤ የበደሉትን ያህል ንስሓ ይገቡ ዘንድ ዘመንን ወስ ነን እንሥራላቸው፤ ንስሓ ቢገቡ ግን አባቶች ልጆቻቸውን እንደ ሚምሩ እንቀበላቸው፡፡

፲፪. ኤጲስ ቆጶሳትና ሌሎች ሹማ ምንት ግን ኀጢአትና ነውር ቢኖ ርባቸው ለሙት ልጅና ለድኃ፣ ለመበለትም እውነት ባይፈርዱ፣ ነገር ግን አራጣና እጅ መንሻ ይቀበሉ ዘንድ በአድልዎ ቢፈ ርዱ እነዚህ ከግብዝነታቸው ጋር ይጠፋሉ፤ ይህም በወንድ ምህ ዐይን ያለውን ጕድፍ ለምን ታያለህ? በዐይንህ ግን ያለውን ምሰሶ ስለምን አትመለ ከትም? ተብሎ በወንጌል እንደ ተጻፈ ነው፡፡

፲፫. ሌሎቹ ይህን ክፉ ሥራ አይተው እንዳይሰነካከሉ እንደ ዚህ ያለ ሥራ በእነርሱ ላይ እንዳይገኝ ኤጲስ ቆጶሳትና ካህ ናት ይጠንቀቁ፤ ክፉዎች ሌሎ ችን ያጠፉ ዘንድ፣ የእግዚአብ ሔር በጎችንም ይበትኑ ዘንድ



ካልአነ፤ወይዝርዉ አባግዐ መርዔቱ ለእግዚአብሔር፤እስመ ኀዳጥ ብኑዕ ያብኅዕ ብዙኀ ሐሪጸ ከማሁ ትተ ልዎሙ ኀጢአት ለእለ ይገብርዋ ከመዝ ፤ ወፈድፋደ ታማስኖሙ ለብዙኃን ከመ ሰራቂ ሶበ ይትረከብ በንዋይ ያወፅእ ስመ እኩየ ላዕለ አዝማዲሁ በእከየ ምግባሩ፤ ወከመ ጽዩዕ ሥጋ ማውታ ሶበ ይትወደይ ውስተ ቅብዕ ይማስን ዜና ጣዕሙ፤ ወከመ ዐማፂ ንጉሥ ወጸዋግ ዘአልቦ ፍትሕ ወከማሁ አንትሙሂ መኳንንቲሁ፤ ወከመ ዝልጉስ በግዕ ሶበ ይትረዐይ ማእከለ አባግዕ ይከውኑ ኵሎሙ ዝልጉሳነ፤ ለእመ ኢተፈልጠ እም ኔሆሙ፣ ወበከመ ከልብ እቡድ ዘይነስክ ኵሎ ዘረከበ እመ ኢቀተ ልዎ የአብዱ ኵሎሙ ዘነሰኮሙ ኅቡረ ምስሌሁ፤ ወከማሁ እመቦ ብእሲ መስተሣልቅ ወመስሐቲ ወመ ስተጋዕዝ ወዐላዊ ትእዛዝ ዘውስተ ሕግ ያውጽእዎ አፍአ እምቤተ ክርስቲያን ከመ ኢያማስን ቤተ እግዚአብሔር፤ ወኢይረሲ በአተ ፈያት፡፡

ምክንያትን ይሻሉና ጥቂት እርሾ ብዙውን ዱቄት ኮምጣጣ ያደር ጋልና፣ እንደዚህም ሁሉ ኀጢአት እንዲህ ለሚሠሯት ትከተላቸ ዋለች፤ ብዙ ሰዎችንም ፈጽማ ትጐዳቸዋለች፤ ሌባ የሰውን ገን ዘብ ሰርቆ በተገኘ ጊዜ በሥ ራው ክፋት በዘመዶቹ ላይ ክፉ ስምን እንደሚያወጣ የሚሸት የበክት ሥጋም በቅባት ውስጥ በተጨመረ ጊዜ የጣዕሙ ሽታ እንደሚጠፋ፣ፍርድ እንደሌለው እንደ ዐመፀኛና ክፉ ንጉሥም እናንተ መምህራንም እንዲሁ ናችሁ፤ የታመመ በግ በበጎች መካከል በተሰማራ ጊዜ ከእ ነርሱ ካልተለየ ሁሉም ሕመ ምተኞች እንደሚሆኑ፣ ያገኘ ውን ሁሉ የሚነክስ ዕብድ ውሻ ካልገደሉት የነከሳቸው ሁሉ በአን ድነት ከእርሱ ጋራ እንደ ሚአብዱ እንዲሁ የሚዘብት፣ የሚያስት፣ ክርክርንም የሚያ መጣ፣ በሕግ ያለውንም ትእ ዛዝ የሚአፈርስ ሰው ቢኖር የእግዚአብሔርን ቤት እንዳያ ጠፋ፣ የቀማኛ ዋሻም እንዳያ ደርግ ከቤተ ክርስቲያን ወደ ውጭ ያውጡት፡፡

፲፬. ኢርቱዕ ናርምም በእንተ ኃጥኣን ወዐማጽያን አላ ንገሥጾሙ ከመ ይኅድጉ ምግባሮሙ ወያስሉ እምኔሆሙ ምግባረ ኀሡመ ወልማደ፤ ዳዕሙ ነአዝዞሙ ይጹሙ፣ ወይጸልዩ፣ ወይመጽውቱ፣ ወከመ ይትመሀሩ ፈሪሀ እግዚአብሔር፤ እስመ ይቤሎሙ ለደቂቀ እስራኤል ፍርሁኒ ፤ ወዕቀቡ ትእዛዝየ[፯] ::

፲፭. መፍትው ለኤጲስ ቆጶስ ይተክዝ በእንተ ኀጢአተ ሕዝቡ፤ ወየሐሊ ለለ፩፩ ሕይወቶሙ ከመ ይኩኖሙ መርሶ መድኃኒት ለምግባረ ጽድቅ፤ ወይኩኑ ድልዋነ ለእግዚአብሐር ወይድኀኑ እምኵነኔ እንተ ትረክቦሙ ለኃጥኣን በዕለተ ደይን::

፲፮. ወእለሰ ይትሀከዩ ይስምዑ በእንተ ዕልዋን ዘይቤ ለምንት አርመምክሙ ወፍሬሆሙ አረርክሙ[፰] ::

፲፬. ስለ ኃጥኣንና ስለ ዐመፀኞች ዝም እንል ዘንድ አይገባንም፤ ነገር ግን ክፉ ሥራቸውን ይተዉ ዘንድ፣ ከእነርሱም ክፉ ሥራንና ልማድን ያስወግዱ ዘንድ እንምክራቸው፤ ይጾሙና ይጸልዩ ይመጸውቱም ዘንድ፣ እግዚአብሔርንም መፍራት ይማሩ ዘንድ እንዘዛቸው፤ የእስራኤልን ልጆች ፍሩኝ፤ ትእዛዜንም ጠብቁ ብሏቸዋልና::

፲፭. ኤጲስ ቆጶሱ ስለ ሕዝቡ ኀጢአት ያዝን ዘንድ ይገባዋል፤ ለጽድቅ ሥራም የመዳን ወደብ ይሆናቸው ዘንድ፣ ለእግዚአብሔርም የተዘጋጁ ይሆኑ ዘንድ፣ በፍርድ ቀን ኃጥኣንን ከምታገኛቸው ፍዳም ይድኑ ዘንድ ለእያንዳንዱ ሕይወታቸውን ያስብ ዘንድ ይገባዋል ::

፲፮. ቸል የሚሉ ግን «ስለ ከዳተኞች ለምን ዝም አላችሁ? ፍሬዎቻቸውንስ ለምን ለቀማችሁ» ያለውን ይሰማሉ::

፯ ዘሌዋ ፲፱ ፡ ፴፯
፰ ሆሴ ፲ ፡ ፲፫



፲፯. ርቱዕ ለኤጲስ ቆጶስ ይርዐዮሙ ለሕዝብ በሰላም፤ ወለእለ ኢአበሱ ኢይኅድጎሙ ይደቂ፤ወለእለሂ አበሱ ይሚጦሙ ውስተ ንስሓ::

፲፰. ስምዑ ዘይቤለክሙ እግዚአብሔር ኤጲስ ቆጶሳት ኢታስትቱ ፩ደ እምእሉ ንኡሳን[፱]፤አላ መፍትው ትስረዩ ወታናኅስዩ ለዘአበሰ ወእምከመ አምነ ኃጥእ በኀጢአቱ፣ ወጸርሐ ኀበ እግዚብሔር እማዕምቀ ልቡ በብካይ ወበገዓር ምስለ ትሕትና ያወሥኦ መንፈስ ቅዱስ ወይቤሎ ሰረየ ለከ እግዚአብሔር ኀጢአተከ[፲] ::

፲፱. አእምር እንከ ኤጲስ ቆጶስ ሚመጠን ጸገወከ እግዚአብሔር ክብረ ወስብሐተ፤ ወወሀበከ ሥልጣነ ትእሥር ወትፍታሕ ዑቅርእሰከ ወዕቀብ መርዔቶ ለክርስቶስ፤ ሑር በፍኖተ ርትዕ እንዘ ሕያው አንተ በዝ ዓለም፤ እስመ ሀለወከ ትትኀሠሥ በዕለተ ኵነኔ እስመ ለዘአዕቀብዎ ብዙኀ፤

፲፯. ሕዝቡን በሰላም ይጠብቃቸው ዘንድ ለኤጲስ ቆጶሱ አግባብ ነው፤ ያልበደሉትንም በኃጢአት ይሰነካከሉ ዘንድ አይተዋቸው፤ የበደሉትንም ወደ ንስሓ ይመልሳቸው::

፲፰.ኤጲስ ቆጶሳት እግዚአብሔር ከእነዚህ ከታናናሾች አንዱን አታቃሉ ያላችሁን ስሙ፤ ነገር ግን ለበደለኛው ኀጢአቱን ታስተሠርዩለትና ታቃልሉለት ዘንድ ይገባል፤ ኃጥእ ኀጢአቱን አምኖ ከትሕትና ጋር በልቅሶ በመጮህ በጥልቅ ልቡ ወደ እግዚአብሔር ቢጮህ መንፈስ ቅዱስ «እግዚአብሔር ኀጢአትህን ይቅር አለህ» ብሎ ይመልስለታል::

፲፱. ኤጲስ ቆጶስ፣ እግዚአብሔር ክብርንና ጌትነትን ምን ያህል እንደሰጠህ ዕወቅ፤ታሥርና ትፈታም ዘንድ ሥልጣንን እንደ ሰጠህ ዕወቅ፤ ራስህን ዕወቅ፣ የክርስቶስን መንጋዎች ጠብቅ፤ አንተ በዚህ ዓለም ሕያው ሳለህ በእውነት መንገድ ሂድ፤ በፍርድ ቀን ትመረመራለህና፤

፱ ማቴ ፲፰ ፡ ፲
፲. ፪ኛ ሳሙ፡ ፲፪ ፡ ፲፫

ብዙኀ ይትሐሠሥዎ[፲፰]፡፡ወእስመ አልቦ ዘየሐዩ ሰብእ ወኢአሐተ ሰዓተ ዘእንበለ ኀጢአት[፲፱]፤ ዘእ ንበለ ፩ዱ ዘኮነ ሰብአ በእንቲአነ እግዚአብሔር ቃል፡፡

፳. ወበእንተዝ ተጽሕፈ ተዝካሮሙ ለጻድቃን እለ የዐቅቡ ርእሶሙ እስመ ይቤ አባግዐየ እሊአየ ይሰምዓኒ ቃልየ፤ ወአነሂ አአምሮን፣ ወእማንቱሰ ይተል ዋኒ፤ ወእሁቦን ሕይወተ ዘለዓለም[፳]፡፡

፳፩. ወይቤ ሕዝቅኤል ነቢይ «አንትሙ አባግዕየ ከመዝ ይቤ እግዚአብሔር አዶናይ ናሁ አነ እፌትሕ ማእከለ በግዕ ወበግዕ፣ ወማእከለ በሐኵ ወማእከለ ዳቤላ፡፡

፳፪. ኢአከለክሙኑ ዘተረዐይ ክሙ ውስተ ሠናይ ጺአት፤ ወዘተርፈኒ ሣዕሮ ትከይዱ በእገሪክሙ ወፅሩየሂ ማየ ትሰ ትዩ ወዘተርፈኒ ተሐምግዎ በእገሪክሙ፡፡

፲፰ ሉቃ ፲፪ : ፵፰
፲፱ ኢዮብ ፲፬ : ፬
፳ ዮሐ ፲-፬

ብዙ አደራ ያስጠበቁትን ብዙ ይፈልጉበታልና፤ ስለ እኛ ሰው ከሆነው ከአንዱ ከእግዚአብሔር ቃል በቀር አንድ ሰዓት ስንኳ ያለ ኀጢአት የሚኖር ሰው የለ ምና፡፡

፳. ስለዚህ ራሳቸውን የሚጠ ብቁ የጻድቃን መታሰቢያቸው ተጻፈ ፤ በጎቼ ቃሌን ይሰሙ ኛል፤ እኔም አውቃቸዋለሁ ፤ እነርሱም ይከተሉኛል ፤ የዘለ ዓለም ሕይወትንም እሰጣቸ ዋለሁ» ብሏልና፡፡

፳፩. ነቢዩ ሕዝቅኤል እንዲህ አለ «እናንተም መንጋዬ ሆይ! እነሆ በበግና በበግ መካከል፣ በአውራ በግና በአውራ ፍየልም መካከል እፈርዳለሁ፣» ይላል ጌታ እግዚአብሔር፡፡

፳፪. የቀረውን ማሰማሪያችሁን በእግራችሁ የረገጣችሁት የተሰ ማራችሁበት መልካሙ መሰማ ሪያ ባይበቃችሁ ነውን፣ የቀረ ውንስ ውኃ በእግራችሁ ያደፈረ ሳችሁትን ጥሩውን ውኃ መጠ ጣታችሁ ባይበቃችሁ ነውን ፡፡



፳፫. ወትርእዩ አባግዕየ ዘኬድ ክሙ በእገሪክሙ ወታስተይዎሙ ማየ ዘሐመግሙ በእገሪክሙ፡፡

፳፬. ወየአምሩ ከመ አነ ውእቱ እግዚአብሔር አምላኮሙ ወእሙ ንቱ ይከውኑኒ ሕዝብየ ቤተ እስ ራኤል ይቤ እግዚአብሔር እግ ዚእ፡፡

፳፭. አንትሙ አባግዐ መርዔ ትየ፤ ወአነ እግዚአብሔር አምላ ክክሙ ይቤ እግዚአብሔር፤

፳፮. ስምዑ ኤጲስ ቆጶሳት ወስ ምዑ ሕዝብ ዘይቤ እግዚአብ ሔር ናሁ እፌትሕ አነ ማእከለ በሐኵ ወዳቤላ ወማእከለ በግዕ ወበግዕ ፡፡

፳፯. ይቤ አነ እፌትሕ ማእከለ ኖሎተ አባግዕ እለ አማሰኑ አባ ግዕየ በሀኬቶሙ[፳፩]፤ ወካዕበ ይቤ አነ እፌትሕ ማእከለ ኤጲስ ቆጶስ ወካልኡ፣ ወማእከለ ሕዝ ባዊ ወሕዝባዊ፣ ወማእከለ መኰ ንን ወመኳንንት እስመ አባግዕየ ነባብያን እሙንቱ፤ ወኢኮኑ ዘእ ንበለ ነቢብ፡፡

፳፩ ሕዝ. ፴፬ : ፲፯ - ፲፱

፳፫. በጎቼም በእግራችሁ በረገ ጣችሁት ይሰማራሉ፤ በእግራች ሁም ያደፈረሳችሁትን ውሀ ይጠጣሉ፡፡

፳፬. እኔ እግዚአብሔር አምላካ ቸው ከእነርሱ ጋር እንዳለሁ እነ ርሱም የእስራኤል ቤት ሕዝቤ እንደሆኑ ያውቃሉ ይላል ጌታ እግዚአብሔር፡፡

፳፭. እናንተም የማሰማሪያዬ በጎች ናችሁ፣ እኔም አምላካ ችሁ ነኝ ይላል ጌታ እግዚአብ ሔር፡፡

፳፮. ኤጲስ ቆጶሳትና ሕዝቡ፣ እግዚአብሔር በአውራውና በአ ውራው መካከል፣ በበግና በበግ መካከልም እነሆ እኔ እፈርዳለሁ ያለውን ስሙ፡፡

፳፯. በስንፍናቸው በጎቼን ባጠፉ በበጎች ጠባቆች መካከል እኔ እፈ ርዳለሁ አለ፤ ሁለተኛም በኤ ጲስ ቆጶሱና በጓደኛው፣ በሕዝ ባዊውና በሕዝባዊው፣ በመኳ ንንትና በመኰንንት መካከል እኔ እፈርዳለሁ አለ፤ በጎቼ የሚናገሩ እንጂ የማይናገሩ አይደሉምና፡፡

፷፰. ወበእንተዝ ኢይበሉ ሕዝብ አባግዕ ንሕነ ወኢኮነ ኖሎተ ዘንትዐቀብ ለርእስነ፤ ለያእምር ዘንተ ኖላዊ እስመ ውእቱ ባሕቲቱ ይትሐተት ከመ ያግብእ ቃለ በእንቲአነ፤ ወከመ በግዕ ዘኢይተሉ ኖላዌ ኄረ ይከውን ለዝዕብ ከመ ይማስን ::

፷፱. ከማሁ ዘይተሉ አብደ ወእኩየ ኖላዌ ይከውን ለሞት እስመ ይውኅጦ ለሊሁ ኖላዊ፣ ወበእንተዝ ርቱዕ ንርኀቅ እምእኩያን ወጕሕላውያን ኖሎት እለ ኢይምሕኩ ወኢያድኅኑ መርዔተ፣ አላ ንትልዎሙ ለኄራን እለ ይምሕኩ ወያድኅኑ መርዔቶሙ::

፸. ወለኖላዊ ኄር ያፈቅርዎ ሕዝብ፤ ወይፈርህዎ ከመ አብ፣ ወእግዚእ፣ ወከመ መምህር፣ ወከመ ሊቀ ካህናቲሁ ለእግዚአብሔር፤ ወውእቱ መገሥጸሙ ወመርሖሙ ውስተ ሠናይ አምልኮ፤እስመ ዘይትኤዘዝ ሎቱ ይትኤዘዞ

፷፰. ስለዚህም ሕዝቡ በጎች ነን እንጂ ለራሳችን የምንጠነቀቅ አይደለም አይበሉ፤ እረኛውም ይህን ይወቅ፤ ስለ እኛ ቃልን ይመልስ ዘንድ እርሱ ብቻውን ይመረመራልና፣ቸር እረኛን የማይከተልም ይጠፋ ዘንድ ለኻርብ እንደሚሆን::

፷፱. እንደዚሁ ሰነፍና ክፉ እረኛን የሚከተል ለሞት ይሆናል፤ ራሱ እረኛው ይውጠዋልና፣ ስለዚህም ከማይራሩና መንጋቸውን ከማያድኑ ከክፉዎችና ከከዳተኞች እንርቅ ዘንድ አግባብ ነው፤ ነገር ግን የሚራሩና መንጋቸውን የሚያድኑ ቸሮች እረኞችን እንከተላቸው::

፸. ቸር እረኛንም ሕዝቡ እንደ አባት፣ እንደ ጌታና፣ እንደ መምህር እንደ ሊቀ ካህናትም ይወዱታል፣ያከብሩታልም፤እርሱም መካሪያቸውና መሪያቸው ነው፤ ለእርሱ የሚታዘዝ ለክርስቶስ ይታዘዛልና፣ ቃሉንም የሚሰማ ክርስቶስን



ለክርስቶስ፤ወዘይሰምዕ ቃሎ ይሰምዖ ለክርስቶስ፤ወዘሰ አበዮ ወኢሰምዐ ቃሎ አበዮ፣ ወዐለዎ ለክርስቶስ፣ ወዘይትኤዘዝ ለክርስቶስ ይትኤዘዞ ለእግዚአብሔር ፤ እስመ ይቤ ዘኪያክሙ ሰምዐ ኪያየ ሰምዐ፤ ወዘለክሙ አበየ ሊተ አበየ፤ ወዘሊተ አበየ አበዮ ለዘፈነወኒ[፲፮] ::

፸፩. ከማሁ ርቱዕ ያፍቅሮሙ ኤጲስ ቆጶስ ለሕዝብ ከመ ደቂቁ እስመ ውሉዱ እሙንቱ፤ወይሕፅኖሙ በተግሣጽ ከመ ዖፍ እንተ ተሐቅፍ አንቆቅሆሃ፤ ወተሐፅን ዕጐሊሃ እስከ ሶበ ይሠርራ፤ ወከማሁ ይምህሮሙ ቃለ እግዚአብሔር ለሕዝብ፤ ወይሴስዮሙ ትምህርተ መንፈሳዊተ፤ ወየሀበሙ ጸሕቆሙ ለኵሎሙ እለ ይፈቅዱ ይንሥኡ በኀቤሁ፤ ወኢያክብድ ዲቤሆሙ፤ አላ ይገሥጾሙ በቃለ ጥበብ ወያፍርሆሙ ከመ ኢይትመየጡ ውስተ ኀጢአት፣ ዳዕሙ የአዝዞሙ ይሑሩ ፍኖተ ርትዕ፤ ወይዕቀቡ ሃይማኖተ፤ ወይርዐዮሙ ለሕዝብ በሰላም ::

ይሰማል፣ እርሱን እንቢ የሚለውና የማይሰማው ግን ክርስቶስን እንቢ ይለዋል፤ ይክደዋልም፤ ለክርስቶስ የሚታዘዝም ለእግዚአብሔር ይታዘዛል፤ እናንተን የሰማ እኔን ሰማ፤ እናንተንም እንቢ ያለ እኔን እንቢ አለ፤ እኔንም እንቢ ያለ የላከኝን እንቢ አለው »ብሏልና::

፸፩. እንደዚሁም ኤጲስ ቆጶሱ ሕዝቡን እንደ ልጆቹ ሊወዳቸው ይገባል፤ እነርሱ ልጆቹ ናቸውና፣ እንቍላሏን እንደምትታቀፍ አድገው እስኪበሩ ድረስም ልጆቿን እንደምታሳድግ ወፍ በምክር ያሳድጋቸው፣ እንደዚሁም የእግዚአብሔርን ቃል ያስተምራቸው መንፈሳዊት ትምህርትንም ይመግባቸው፤ ከእርሱም ይቀበሉ ዘንድ ለሚወዱት ሁሉ ፍላጎታቸውን ይስጣቸው፤ በነርሱም ላይ ሥርዐትን አያክብድባቸው፤ በጥበብ ቃል ይምከራቸው እንጂ፣ ወደ ኀጢአትም እንዳይመለሱ ያስፈራራቸው፤ በእውነት ጎዳና ብቻ ይሄዱ ዘንድ፣ ሃይማኖትንም ይጠብቁ ዘንድ ይዘዛቸው፤ ሕዝቡንም በሰላም ይጠብቃቸው::

[፲፮] ሉቃ ፲ ፡ ፲፮

፴፪. ወዓዲ ያንሥኡሙ ለውዱቃን፤ ወያጽንዕዎሙ ለድኩማን፤ ወያስተጋብኡሙ ለዝርዋን፤ ወይፈውሶሙ ለቍሱላን፤ ወይናዝዞሙ ለዕንቡዛነ ልብ፤ ወያጽንዕዎሙ ለሐንካሳን በቃለ ተግሣጽ፤ ወያቅልል ፃረ ክበደ ኀጢአቶሙ፤ ከመ ይርከቡ ተስፋ ሠናየ ።

፴፫. ወእሙንቱሰ ይትመሀሩ ሕገ ቤተ ክርስቲያን፤ ወይትመየጡ ውስተ ንስሓ ወእመቦ ዘተገድፈ አፍአ በኢለብዎ ቃለ መጻሕፍት፤ ኢትመንኖ ወኢትኅድጎ ይድኀጽ ውስተ ኀጢአት፤ አላ ርድኦ፤ ወፈውሶ እምቍስለ ኀጢአት፤ወሚጦ ኀቤከ፤ ወአግብኦ ውስተ መርዔተ ክርስቶስ፤ ወዘሰ አበየ ተመዪጦ ይወፅእ እመርዔትከ ፤ ወይከውን መብልዐ ለአዕዋፈ ሰማይ ወለአራዊተ ገዳም፤ ወይከውን መክፈልቱ ምስለ እለ ይብሉ ንብላዕ ወንስተይ ወጌሠመ ንመውት[፲፮]፤ ወኢይሔልዩ ደኃሪቶሙ።

፲፮ ፩ቆሮ ፲፭ ፡ ፴፫

፴፪. ዳግመኛም የወደቁትን ያንሣቸው፤ የደከሙትንም ያጽናቸው፤ የተበተኑትንም ይሰብስባቸው፤ የቈሰሉትንም ያድናቸው፤ አእምሮ ያጡትንም ያረጋጋቸው፤ የሚያነክሱትንም በተግሣጽ ቃል ያጽናቸው፤ በጎውን ተስፋ ያገኙ ዘንድ የኀጢአታቸውን የክብደት ጽናት ሸክም ያቃልልላቸው።

፴፫. እነሱ ግን የቤተ ክርስቲያንን ሥርዐት ተምረው ወደ ንስሓ ይመለሱ፤ የመጻሕፍትን ቃል ባለማስተዋል በውጭ የወደቀ ቢኖር በኀጢአት ይሰነካከል ዘንድ ቸል ብለህ አትተወው፤ ነገር ግን ረድተህ ከኀጢአት ቍስል አድነው ፤ ወደ አንተም መልሰው ፤ ወደ ክርስቶስም መንጋ አግባው ፤ መመለስን እንቢ የሚል ግን ከመንጋዎችህ ይወጣል፤ ለሰማይ ወፎችና ለዱር አራዊት መብል ይሆናል፤ እድል ፈንታውም እንብላ፤ እንጠጣ፤ ነገም እንሞታለን ከሚሉና ፍጻሜያቸውን ከማያስቡ ሰዎች ጋር ይሆናል።



፴፬. ወእመቦ ዘርእየ ኤጲስ ቆጶስ እንዘ ከመዝ ይገብር ርቱዕ ይበሎ አነ እፀውር ኀጢአተከ፤ ወእመውት ህየንቴከ በከመ ሞተ ክርስቶስ በእንተ ኀጢአተ ዓለም፤ ወእምዝ ይጸሙ፤ ወይሕምም ምስሌሁ እስከ ይትመየጥ ኀበ ንስሓ እስመ ኖላዊ ኄር ይሜጡ ነፍሶ ቤዛ አባግዒሁ።

፴፭. ወዐሳብሰ ዘኢኮነ ኖላዌ፤ወዘኢኮና አባግዕ ዘዚአሁ ሶበ ይሬኢ ተኵላ እንዘ ይመጽእ ይጐይይ፤ ወየኀድግ አባግዒሁ፤ወይመስጦን ተኵላ፤ ወይዘርዎን ለአባግዒሁ፤ እስመ ዐሳብ ውእቱ፤ ወኢየኀዝን በእንተ አባግዕ[፲፯] ።

፴፮. ርቱዕ ናእምር ከመ እግዚአብሔር መሐሪ ውእቱ፤ወኢይፈቅድ ሞቶ ለኃጥእ፤አላ ሚጠቶ ወግብአቶ ውስተ ንስሓ።

፴፯. ወእመቦ ዘይኤብስ በኢለብዎ ዘሥርዐ እግዚአብሔር ትእዛዛቲሁ ለንስሓ ወየሐውር በጽልሑተ ልቡ ወኢይዜክር ኀጢአቶ ወእከዮ

፲፯ ዮሐ ፲ ፡ ፲፪

፴፬. ኤጲስ ቆጶሱ እንደዚህ ሲያደርግ ያየው ቢኖር ኀጢአትህን እኔ እሸከማለሁ፤ ክርስቶስ ስለ ዓለም ኀጢአት እንደሞተም ስለ አንተ እሞታለሁ ይበለው፤ ከዚህ በኋላ ወደ ንስሐ እስኪመለስ ድረስ ከእርሱ ጋራ ይድከም፤ መከራንም ይቀበል፤ ቸር እረኛ ስለ በጎቹ ቤዛ ሆኖ ሰውነቱን አሳልፎ ይሰጣልና።

፴፭. እረኛ ያይደለ፤ በጎቹም የርሱ ያልሆኑ ምንደኛ ግን ተኵላ ሲመጣ ባየ ጊዜ በጎቹን ትቶ ይሸሻል፤ ተኵላም በጎችን ይነጥቃቸዋል፤ ይበትናቸዋልም፤ ምንደኛ ነውና ስለ በጎች ጥፋትም አያዝንም።

፴፮. እግዚአብሔር ቸር እንደሆነ፤ የኀጢአተኛውንም ሞት እንደማይወድ፤ እናውቅ ዘንድ ይገባል፤ ወደ ንስሓ ፈጽሞ መመለሱን ነው እንጂ።

፴፯. እግዚአብሔር ለንስሓ የሠራቸውን ትእዛዞቹን ባለማወቅ የሚበድል ሰው ቢኖር በልቡናውም ተንኰል ቢሄድ፤የእርሱን ቸርነት

ዘገብረ ኢተዘኪሮ ቃለ ቅዱሳት መጻሕፍት ዘዜነዋ ምሕረተ ዚአሁ ይማስን ውእቱ ብእሲ፤ ወይከውን ዘአልቦቱ ተስፋ።

፴፰. ወአንተሰ ኃሥሥ ኖላዌ ኄረ፣ ወመምህረ የዋህ፣ ወመገሥጸ፣ ወዕጉሠ፣ ወመሐሬ፣ ወገባሬ ሰላም፣ ዘየዐውድ፣ ወይርዒ አባግዒሁ፣ ወየኃሥሥ ዘተገድፈ ፤ ከመ እግዚአብሔር አምላክነ እስመ አቡነ ዘበሰማያት ፈነወ ወልዶ ፍቁረ መድኀኒነ ኖላዌ ኄረ፣ ወመምህረ ኢየሱስሃ ክርስቶስሃ ዘኀደገ ፺ ወ፱ተ ውስተ ገዳም፣ ወሖረ ይኅሥሥ በግዐ ዘተገድፈ፣ ወሶበ ረከቦ ጾሮ ዲበ መትከፍቱ ወአብኦ ውስተ መርዔት በፍሥሐ እስመ ረከበ ዘተሀጕለ[፲፰]።

፴፱.ስማዕ ዘንተ ኤጲስ ቆጶስ፤ ምርሖሙ ለእለ ስሕቱ እምፍኖት ርትዕት፤ ወአስተጋብኦሙ ለእለ ተዘርዉ፤ ወኃሥሦሙ ለእለ ተገድፉ እስመ ብከ ሥልጣን ለሚጠት ትእሥር ወትፍታሕ፤ እስመ ይቤሎ መድኀኒነ

የሚናገሩ የቅዱሳት መጻሕፍትን ቃል ሳያስተውል የሠራውን ክፋት፣ ኀጢአቱንም ባያስብ ያ ሰው ይጠፋል፤ ተስፋ የሌለውም ይሆናል።

፴፰. አንተ ግን ቸርና አስተማሪ፣ የሚገሥጽና የሚራራ፣ የሚታገሥና ሰላምን የሚያደርግ፣ እየዞረ በጎችን የሚጠብቅ እንደ ፈጣሪያችን እንደ እግዚአብሔር የጠፋውን የሚፈልግ እረኛን ፈልግ፤ ሰማያዊ አባታችን የተወደደ፣ መድኀኒታችን ቸር ጠባቂና መምህር ዘጠና ዘጠኙን በዱር ትቶ የጠፋውን በግ ይፈልግ ዘንድ የሄደ ልጁ ኢየሱስ ክርስቶስን ልኳልና፤እርሱም ባገኘው ጊዜ በትከሻው ተሸክመው በደስታም ወደ መንጋው መለሰው፤ የጠፋውን አግኝቷልና።

፴፱. ኤጲስ ቆጶስ ሆይ! ይህን ስማ፤ ከቀናች መንገድ የተሳሳቱትን ምራቸው፤ የተበተኑትንም ሰብስባቸው፤የጠፉትንም ፈልጋቸው፤ ለመመለስ ታስርና ትፈታ ዘንድ ሥልጣን አለህና፣ መድኃኒታችን መፃጉዕን

፲፰ ሉቃ ፲፭ : ፬ - ፯



ለመፃጉዕ ኀደጉ ለከ ኀጢአተከ፤ ሃይማኖትከ አሕየወተከ፤ ሑር በሰላም[፲፱] ፤ ወሰላም ዘተመጦነ ይእቲ ቤተ ክርስቲያኑ ለክርስቶስ እንተ ታበውእ ውስቴታ እለ ነስሑ ወነጽሑ እምኀጣውኢሆሙ፤ ወገብሩ ጽድቀ ወሠናየ፤ ወረከቡ ተስፋ ሕይወት።

፵. መፍትው ለኤጲስ ቆጶስ ይፈውስ ዱያነ እለ ደወዩ በገቢረ ኀጢአት ፤ የሐውጾሙ ወይናዝዞሙ፤ ወይፈውስ ቊስሎሙ፤ እስመ አኮ ጥዑያን ዘይፈቅድዎ ለዐቃቤ ሥራይ፣ አላ ሕሙማን እስመ መጽአ ወልደ ዕጓለ እመ ሕያው ይኅሥሥ፣ ወይርዳእ ዘተሀጕለ[፳]፤እስመ አንተኒ ዐቃቤ ስራይ በውስተ ቤተ ክርስቲያኑ ለእግዚአብሔር፤ ሀቦሙ ፈውሰ ለለ፩፩ በከመ ይደሉ ወሴስዮሙ ሲሲተ መንፈሳዊተ ይጽንዑ በቅድስት ቤተ ክርስቲያን።

«ኀጢአትህን ይቅር ብየሃለሁ፣ ሃይማኖትህ አዳነችህ፣ በሰላም ሂድ» ብሎታልና፤ የተቀበልናት ሰላምም ንስሓ ገብተው ከኀጢአታቸው የነጹትን፣ ጽድቅንና በጎ ሥራን የሠሩትን፣ የሕይወት ተስፋንም ያገኙትን ወደ እርስዋ የምታስገባ የክርስቶስ ቤተ ክርስቲያን ናት።

፵. ለኤጲስ ቆጶስ ኀጢአት በመሥራት የታመሙ ድውያንን ያድን ዘንድ ፣ ይጐበኛቸውና ያጽናናቸው፣ቊስላቸውንም ያድናቸው ዘንድ ይገባዋል፤ ባለመድኀኒትን የሚሹት ሕመምተኞች ናቸው እንጂ ጤነኞች አይደሉምና፣ የሰው ልጅ የጠፋውን ሊፈልግና የተጐዳውን ሊረዳ መጥቶአልና፣ አንተም በእግዚአብሔር ቤተክርስቲያን ውስጥ ባለመድኀኒት ስለሆንክ ለእያንዳንዱ እንደሚገባ ፈውስን ስጣቸው፤ በቅድስት ቤተ ክርስቲያንም ይጸኑ ዘንድ መንፈሳዊ ምግብን ስጣቸው።

፲፱ ሉቃ ፯ : ፲፰ ፤ ማር ፪ : ፯ : ፲፩
፳. ማቴ: ፱. ፲፪

፵፩. ወረዐይ መርዔቶ ለክርስቶስ በትሕትና ወበፍቅር ዘእንበለ መዓት ወእንዘ ኢትትዔበይ በሢመተ ሥልጣንከ እስመ አንተ ኖላዌ መርዔቱ ለክርስቶስ፣ ወአስተጋብኦሙ ለመሐስዓን ውስተ ሕፅንከ ።

፵፪. ኩንኬ መሐሬ ወጻድቀ ዘእንበለ ጽልሑት ወቂም፣ ወቅንአት፣ ወውዴት፣ወሐሜት፣ወጽልእ፣ወአድልዎ፣ወፅርፈት፣ወትዕቢት፣ወትምክሕት፣ ወኢትመንኖሙ ለእለ እምታሕቴከ፣ ወኢትኅባእ እምኔሆሙ ትእዛዛቲሁ ለእግዚአብሔር ወኢትትመየጥ እምንስሐሆሙ ወኢታምጽእ ምክንያተ ላዕሌሆሙ ወኢታርኅቆሙ እምቤተ ክርስቲያን።

፵፫. ለቡ እንከ ፍትሐ፤ ወኢትንሣእ እንከ ስምዐ ፩ደ ወኢላዕለ መኑሂ ዘእንበለ ስምዐ ፪ቱ ኄራን መሐይምናን[፵፩]፣ ወስምዐ ይኩኑ ላዕሌሆሙ ካልኣን ኄራን መሐይምናን እሙንቱ እለ አልቦሙ ጽልእ ወቂም ወቅንዓት እስመ ቦ እምኔሆሙ ነባብያን ሐሰት

፵፩. የክርስቶስን መንጋዎች ሳትቈጣ፣ በሥልጣንህም ሹመት ሳትታበይ በትሕትናና በፍቅር ጠብቅ፤ የክርስቶስ መንጋዎች ጠባቂ አንተ ነህና፣ ጠቦቶቹንም ወደ አጠገብህ ሰብስባቸው ።

፵፪. ያለ ሽንገላና ያለ ቂም፣ ያለ ቅንአትና ያለ ነገር ሥራ፣ ያለ ሐሜትና ያለጥል፣ ያለ አድልዎና ያለስድብ፣ ያለትዕቢትና ያለትምክሕት፣ የምትምር እውነተኛ ሁን፤ ከበታችህ ያሉትን አትናቃቸው የእግዚአብሔርን ትእዛዞች ከእነርሱ አትሠውር፤ ከንስሐቸውም ዘወር አትበል፤ በላያቸውም ምክንያትን አታምጣ፤ ከቤተ ክርስቲያንም አታርቃቸው።

፵፫. እንግዲህ ፍርድን አስተውል፤ ደጋጎች ምእመናን ከሆኑ ከሦስት ሰዎች ምስክርነት በቀር በማንም ላይ የአንድ ሰው ምስክርነት አትቀበል፤በእነርሱም ላይ ጥልና ቂም ቅንኣትም የሌላቸው ሌሎች ደጋጎች ምእመናን ምስክር ይሁኑ ፤ ከእነርሱ ወገን እንደበታቸው ሁለት ወይም ሦስት የሆነ ፣

---

፵፩. ፩ ጢሞ. ፭. ፲፱



እለ ፪ቱ ወ፫ቱ ልሳኖሙ እለ ይትፌሥሑ በእኩይ ምግባር፣ ወጸላእያነ አኀው ወእለ ይፈቅዱ ይዝርዉ መርዔቶ ለክርስቶስ።

፵፬. ወእመሰ ሰማዕከ ቃሎሙ ወአመንከ ለእለ ይገብሩ ከመዝ ናሁኬ ዘረውከ መርዔተከ ዘእንበለ ፍትሕ ወመጠውኮሙ ለእኩያን አዝዕብት ወመሰጥ፣ ወእሉ እሙንቱ እኩያን ሰብእ ወባሕቱ ኢኮኑ ሰብአ አላ እኩያን አራዊት እለ ይትሜሰሉ ሰብአ ዕልዋነ ወመናፍቃነ ወከሐድያነ እለ ኢየአምርዎ ለእግዚአብሔር፣ እሉኬ ጸናሕያነ ፍኖት ከመ ዝዕብ ዘይመስጥ ወይበልዕ ይመስጡ እለ ይወፅኡ እምሕገ ቤተ ክርስቲያን ።

፵፭. ወሶበ ርእዩ ዘተኀጕለ ይመስሎሙ ዘረከቡ ዐቢየ ረባሐ ለርእሶሙ፣ እስመ አቡሆሙ ዲያብሎስ ቀታሌ ነፍስ ሰብእ ውእቱ።

፵፮. ወለእለሰ ይስሕቱ እምቤተ ክርስቲያን፣ወይወፅኡ እምሕግ ይሬእይዎሙ አጋንንት፣ ወየሐምምዎሙ በፃዕር ፣ ወበምንዳቤ ወኀዘነ ልብ ፣ ወእሙንቱሰ ይተልዉ

በክፉ ሥራም ደስ የሚሰኙ ወንድሞችን የሚጠሉ፣ የክርስቶስን መንጋዎች ሊበትኑ የሚወዱ ሐሰት ተናጋሪዎች አሉና።

፵፬.እንደዚህ የሚያደርጉትን ቃላቸውን ሰምተህ ብታምን እነሆ መንጋዎችህን ያለ ፍርድ በተንህ፤ ለሚነጥቁ ክፉዎች ጅቦችም ሰጠሃቸው ፤ እነዚህም ክፉዎች ሰዎች ናቸው፣ ነገር ግን ሰዎች አይደሉም፤ እግዚአብሔርን የማያውቁ፣ ከዳተኞችና ከሐዲዎች ሰዎችን የሚመስሉ ክፉዎች አውሬዎች ናቸው እንጂ፣ እነዚህም ነጥቆ እንደሚበላ ጅብ ከቤተ ክርስቲያን ሕግ የሚወጡትን ይነጥቃሉ።

፵፭. የጠፋውንም ባዩ ጊዜ ለራሳቸው ታላቅ ረብሕ ያገኙ ይመስላቸዋል፤ አባታቸው ዲያብሎስ ነፍስ ገዳይ ነውና ።

፵፮. ከቤተ ክርስቲያን የሚስቱትንና ከሕግ የሚወጡትን አጋንንት ተመልክተው በጭንቅና በመከራ በልብ ኀዘንም ያሰቃዩዋቸዋል፤ እነርሱ ግን የወንጀለኞችን

ፍኖቶሙ ለዕልዋን ወየሀጒሉ ዕሤቶሙ ወፈድፋደ ይርኅቁ እምእግዚአብሔር ወኤጲስ ቆጶስ ለእመ ኢፈትሐ በርትዕ ይከውን መክፈልቱ ምስሌሆሙ::

፶፯. ኦ ኤጲስ ቆጶስ! ኢመፍትው ኬ ትስድዶ ለኃጥእ፣ ወኢትመንኖ ለዘይትመየጥ፣ ወኢትኩን ሕፁፀ ምሕረት ከመ ትፈውስ ቍስለ ኀጢአት፣ ወኢትትሀወል ምስለ ብእሴ ደም፤ እስመ በእንቲአሆሙ ይብል መጽሐፍ በሊህ እገሪሆሙ ለክዒወ ደም፤ ኀሣር ወቅጥቃጤ ውስተ ፍኖቶሙ ወኢየአምርዋ ለፍኖተ ሰላም፤ ወአልቦ ፍርሀተ እግዚአብሔር ቅድመ አዕይንቲሆሙ[፴፪] ::

፶፰. ፍኖተ ሰላምኒ መድኀኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ ዘመሀረነ እንዘ ይብል ስረዩ ከመ ይስረይ ለክሙ ወሀቡ ወይሁበክሙ ፤ ዘውእቱ ብሂል ኅድጉ ለሰብእ አበሳሆሙ ከመ ይኅድግ ለክሙ አቡክሙ

ኀዳና ይከተላሉ፤ ዋጋቸውንም ያጣሉ፤ ይልቁንም ከእግዚአብሔር ይርቃሉ፤ ኤጲስ ቆጶሱም በቅንነት ባይፈርድ እድል ፈንታው ከእነርሱ ጋራ ይሆናል::

፶፯. ኤጲስ ቆጶስ ሆይ! ኀጢአተኛውን ታባርረው ዘንድ አግባብ አይደለም፤ የሚመለሰውንም አትናቀው፤ የኀጢአትን ቍስል ታድን ዘንድ ምሕረት የጐደለህ አትሁን፤ ከደም አፍሳሽ ሰው ጋርም አትተባበር፤ መጽሐፍ ስለ እርሱ ደምን ለማፍሰስ እግራቸው ፈጣን ነው፤ በመንገዳቸውም ጥፋትና ጒስቊልና አለ፣ የሰላም መንገድንም አያውቋትም፤ በፊታቸው እግዚአብሔርን መፍራት የለም ብሏልና::

፶፰. የሰላም መንገድም፣ ይቅር እንዲላችሁ ይቅር በሉ፤ ስጡ ይሰጣችኋል ብሎ ያስተማረን መድኀኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ነው፣ ይኸውም ሰማያዊ አባታችሁ በደላችሁን ይቅር ይላችሁ ዘንድ እናንተም የሰዎችን በደል

፴፪ መዝ ፴፫ : ፲፬ - ፲፭



ሰማያዊ አበሳክሙ[፴፫] ወዓዲ መሀረነ በጸሎት እንዘ ይብል ኅድግ ለነ አበሳነ ወጌጋየነ ከመ ንሕነኒ ንኅድግ ለዘአበሰ ለነ::

፶፱. ወእመሰ ኢትክሉ አንትሙ ትስረዩ አበሳ ለዘአበሰ ለክሙ፣ በእፎ አንትሙ ትረክቡ ስርየተ አበሳክሙ::

፷. ወእመሰቦ ዘተሰደ ዘእንበለ አበሳ፣ወእምዝ ገቢኦ ሰአለ ስርየተ ወዘኢተወክፎ ዝኬውእቱ ቀታሌ እኁሁ፤ወከዐዊ ደም ከመ ቃየል ዘከዐወ ደመ አቤል እኍሁ፤ ወጸርሐ ደሙ ኀበ እግዚአብሔር[፴፬] ወእመቦ ኤጲስ ቆጶስ ዘሰደደ ሰብአ ዘእንበለ አበሳ ይከውን ከመ ቃየል ቀታሊ::

## አንቀጽ ፯

ከመ ኢመፍትው ንገሥጽ ወኢመነኒ ዘእንበለ ያቅሙ ሎቱ ስምዐ ከመ አበሰ::

ይቅር በሉ ማለት ነው፣ ዳግመኛም በጸሎት እኛ የበደለንን ይቅር እንል ዘንድ በደላችንንና ኃጢአታችንን ይቅር በለን በሉ እያለ አስተማረን::

፶፱. እናንተ የበደላችሁን ሰው በደል ይቅር ትሉ ዘንድ ካልቻላችሁ እናንተ የኀጢአታችሁን ስርየት እንዴት ታገኛላችሁ?

፷. ያልበደለ፣ የተሰደደ ሰው ቢኖር፣ ከዚህም በኋላ ተመልሶ ይቅርታን ቢጠይቅ የማይቀበል ሰው ይህ ወንድሙን ገዳይ ነው፤ የወንድሙ የአቤልን ደም እንዳፈሰሰ፣ ደሙም ወደ እግዚአብሔር እንደጮኸበት እንደ ቃየልም ደም አፍሳሽ ነው፤ ያልበደለ ሰውን ያባረረ ኤጲስ ቆጶስም ቢኖር እንደ ነፍሰ ገዳዩ እንደ ቃየል ይሆናል::

## ሰባተኛ አንቀጽ

እንደ በደለ ሳያስመሰክሩ ማንንም እንቀጣ ዘንድ እንዳይገባ ይናገራል:

፴፫ ማቴ ፮ : ፲፪ ፣ ፲፬
፴፬ ዘፍ ፬ : ፲

፩. ዘይሰድድ ዘእንበለ አበሳ ውእቱ የአኪ እምቀታሌ ነፍስ፤ ወኢይሬኢ ምሕረተ እግዚአብሔር እስመ ኢተዘከረ ፍቅረ ቢጹ።

፪. ወዘይገብር ከመዝ ኢይረክብ መድኀኒተ እስመ ድኀፀ ወወድቀ ውስተ ዐቢይ ኀጢአት፤ ወኢገሠ ጸሙ፤ወኢሜጠሙ ለዘገብሩ ኀጢአተ ብዙኀ፤ አላ ዘረወ መርዔቶ ለእግዚአብሔር እንዘ ይትቃረኖ።

፫. እስመ ጻድቅ እግዚአብሔር ወጽድቅ ኵነኔሁ ወይፈትሕ በጽድቅ ለኵሉ፤ ለጻድቃን ወለኃጥኣን ወመሐሪ ለእለ ይትመየጡ ኀቤሁ፣ ጽድቅ ወምሕረት ወየውሃት ዚአሁ እሙንቱ እስመ ዳዊት ብእሲ ፍቁር ዘከመ ልቡ ለእግዚአብሔር አጠየቀ ከመ ምሕረት ወርትዕ ዚአሁ እሙንቱ።

፬. መፍትውኬ ለኤጲስ ቆጶስ ይፍታሕ በርትዕ፤ወይደልዎ ይግበር ሥምረቶ ለእግዚአብሔር ፤ እስመ እግዚአብሔር ይፈትሕ በርትዕ ለእለ ይትመየጡ ኀቤሁ።

፩.ያልበደለውን የሚያሳድድ ሰው ከነፍስ ገዳይ ይከፋል፤ የእግዚአብሔርንም ምሕረት አያይም፤ የባልንጀራውን ፍቅር አላሰበምና።

፪. እንዲህ የሚያደርግም ድኅነትን አያገኝም፤ በፍጹም ኀጢኣት ተሰነካክሎ ወድቋልና፣ ብዙ ኀጢአት የሠሩትን አልመከራቸውም፣ አልመለሳቸውምም፤ እርሱን እየተቃወመ የእግዚአብሔርን መንጋዎች ይበትናልና።

፫. እግዚአብሔር ጻድቅ ነውና፣ ፍርዱም እውነት ነውና፣ ለጻድቃንና ለኃጥኣንም ሁሉ በእውነት ይፈርዳልና፣ ለሚመለሱትም ይቅር ባይ ነው፤ ምሕረትና ጽድቅ፣ ፍትሕም የእርሱ ገንዘቦች እንደሆኑ እንደ እግዚአብሔር ልብ የሆነው ሰው ዳዊት አስረድቶአል።

፬. ለኤጲስ ቆጶስ በእውነት ይፈርድ ዘንድ አግባብ ነው፤ የእግዚአብሔርን ፈቃድም ይሠራ ዘንድ ይገባዋል፤ በንስሓ ወደ እርሱ ለሚመለሱ ሰዎች እግዚአብሔር በእውነት ይፈርዳልና።



፭. ኢትዜከርኑ ዳዊትሃ አመ አበሰ፤ ወይቤሎ ናታን «ለምንት ገበርከ ከመዝ» ወይቤሎ አበስኩ እንከ፤ ወእኔስሕ፤ ወሶበ አምነ ጌጋዮ ድኅነ እሞት።

፮. ወይቤሎ ናታን «ጽናዕ፤ ወኢትፍራህ እንከ፤ ወኢትመውት[፩]»፤

፯. ወዮናስሂ ነቢይ እንዘ ኢይፈቅድ ይስብክ ሎሙ ለሰብአ ነነዌ ሶበ አበሰ ተሰጥመ ውስተ ባሕር፤ ወውኅጦ አንበሪ ዐቢይ።

፰. ወእምዝ ወፅአ እምከርሠ አንበሪ ወድኅነ እሞት[፪] ።

፱. ወሕዝቅያስኒ ሶበ አልዐለ ልቦኮነ ላዕሌሁ መቅሠፍት ወተትሕተ ሕዝቅያስ፤ ወኀደገ አልዕሎ ልቡ፤ ወበከየ ቅድመ እግዚአብሔር፤ ወመሐሮ[፫] ።

፲. ስምዑ ኤጲስ ቆጶሳት በቍዔተ ዘይከውን ለዝንቱ ግብር፤ እስመ ጽሑፍ ውስተ ራብዕ መጽሐፈ ነገሥት ዘይብል«ሞተ ሕዝቅያስ፤ ወነ ' ምናሴ ወልዱ ህየንቴሁ ፲ወ፪ ክረምቱ ለምናሴ አመ ይነግሥ »።

፭. ዳዊትን አታስብምን በበደለ ጊዜ ናታንም ለምን እንዲህ አደረግህ» ባለው ጊዜ በደልኩ እንግዲህ» ወዲህ ንስሓ እገባለሁ አለው፣ በደሉንም ባመነ ጊዜ ከሞት ዳነ።

፮.ናታንም ጽና አትፍራ፤ እንግዲህ ወዲህ አትሞትም አለው።

፯.ነቢዩ ዮናስም የነነዌን ሰዎች ያስተምራቸው ዘንድ ሳይወድ በበደለ ጊዜ በባሕር ውስጥ ተሰጠመ፤ ታላቅ ዓሣ አንበሪም ዋጠው ።

፰. ከዚህ በኋላ ከዓሣ አንበሪው ሆድ ወጥቶ ከሞት ዳነ።

፱.ሕዝቅያስም ልቡናውን በትዕቢት ከፍ ከፍ ባደረገ ጊዜ በእርሱ ላይ መቅሠፍት መጣበት፤ ሕዝቅያስም ተዋረደ፤ ልቡናውንም በትዕቢት ከፍ ከፍ ማድረግን ተወ፤ በእግዚአብሔርም ፊት አለቀሰ፤ ማረውም።

፲. ኤጲስ ቆጶሳት ለዚህ ሥራ የሚሆነውን ጥቅምን ስሙ፤ በአራተኛው በነገሥት መጽሐፍ እንዲህ የሚል ተጽፏልና፣ ሕዝቅያስ ሞተ፤ በእርሱም ፋንታ ልጁ ምናሴ ነገሠ፤ በነገሠም ጊዜ የምናሴ ዕድሜው ዐሥራ ሁለት ዓመት ነበረ።

፩ ፪ ሳሙ· ፲፪ : ፲፫
፪ ዮናስ ፪ - ፲፩
፫ ፪ ዜና መ. ፴፪ : ፳፭ - ፳፮

፲፩. ወ፺ወ፫ተ ክረምተ ነግሠ በኢየሩሳሌም፤ ወስማ ለእሙ አፍሲባ፤ ወገብረ እኩየ ቅድመ አዕይንቲሁ ለእግዚአብሔር ::

፲፪. ወዓዲ ጽሑፍ ውስተ ዳግም ሕፁፃን ዘይብል «ወገብረ እኩየ ቅድመ እግዚአብሔር እምኵሉ ርኵሶሙ ለአሕዛብ እለ ሠረ ዎሙ እግዚአብሔር እምቅድመ አዕይንቲሆሙ ለደቂቀ እስራኤል»::

፲፫. ወተመይጠ፤ ወሐነፀ አህጉረ ዘነሠተ ሕዝቅያስ አቡሁ፤ ወአ ቀመ አዕማደ ለበዓሊም ::

፲፬. ወገብረ አዕዋመ ወሰገደ በቅ ድመ ኵሉ ተአምራተ ሰማይ፤ወተ ቀንየ ሎሙ፤ ወሐነፀ ምሥዋዐ በቤተ እግዚአብሔር በኀበ ይቤ እግዚአብሔር በኢየሩሳሌም የሀሉ ስምየ ለዓለም ወሐነፀ ምሥዋዐ ለኵሉ ተአምራተ ሰማይ በክ ልኤሆን አዕፃዳተ ቤተ እግዚአ ብሔር::

፲፩. በኢየሩሳሌምም ሃምሳ አም ስት ዘመን ነገሠ፤ የእናቱም ስም አፍሲባ ይባላል፤ በእግ ዚአብሔርም ዐይኖች ፊት ክፉ ሥራን ሠራ ::

፲፪. ዳግመኛም በሁለተኛው ሕፁ ፃን እንዲህ የሚል ተጽፏል «እግ ዚአብሔር በእስራኤል ልጆች ዐይን ፊት ካጠፋቸው ከአሕዛብ ርኵሰት ሁሉ ይልቅ በእግዚአ ብሔር ፊት ክፉ ሥራን ሠራ»::

፲፫. ተመልሶም አባቱ ሕዝቅያስ በአፈረሰው ላይ መሠዊያን ሠራ፤ ለጣዖቱም ዐምዶችን አቆመ::

፲፬. የማምለኪያ ዐፀዶችንም ተከለ፤ በሰማይም ሠራዊት ሁሉ ፊት ሰገደ አመለካቸውም፤ ተገዛላ ቸውም፤ እግዚአብሔር በኢየሩሳ ሌም ስሜ ለዘለዓለም ይኖራል ባለበት በእግዚአብሐር ቤት የጣዖት መሠዊያን ሠራ፤ በሁ ለቱ በእግዚአብሔር ቤት አደባ ባዮች ላይ በሰማይ ከዋክብት አምሳል ለተሠራ ጣዖት ሁሉ መሠዊያን ሠራ ::



፲፭. ወውእቱኒ አውዐየ ውሉዶ በእሳት በቈላተ ወልደ ሄኖም፤ ወያስተቃስም ወያሰግል ወገብረ ቴሌመ፤ወአስተጋብአ ማእምራነ፤ ወማርያተ፤ ወአብዝኀ ገቢረ እከይ ቅድመ እግዚአብሔር ከመ ያም ዕዖ ::

፲፮. ወአንበረ ምስለ ግልፎ ወስ ብኮ በቤተ እግዚአብሔር በኀበ ይቤሎሙ እግዚአብሔር ለዳዊት ወለሰሎሞን ወልዱ በዝንቱ ቤት ወበኢየሩሳሌም ዘኀረይኩ እም ኵሉ ነገደ እስራኤል እሠይም ስምየ ውስቴቱ ለዓለም::

፲፯. ወኢይደግም እንከ አፍልሶተ እግሮሙ ለእስራኤል እምዛቲ ምድር እንተ ወሀብክዎሙ ለአበዊሆሙ፤ ወባሕቱ እመ ዐቀቡ ወገብሩ ኵሎ ዘአዘዝክዎሙ በከመ ጽሑፍ በው ስተ ሕግየ ወትእዛዝየ ወኵነኔ ዚአየ ዘበእዴሁ ለሙሴ::

፲፰. ወአስሐቶሙ ምናሴ ለሕዝበ ይሁዳ ወለኵሎሙ እለ ይነብሩ ኢየሩሳሌም ከመ ይግበሩ ፈድ ፋደ እኪተ እምኵሎሙ አሕዛብ እለ ነጽሖሙ እግዚአብሔር እምቅድመ ገጸሙ ለደቂቀ እስ ራኤል::

፲፭. እርሱም በሄኖም ልጅ ሸለቆ ልጆቹን በእሳት አቃጠለ፤ ሞራ ገላጭም ሆነ፤ አስማትም አደረገ፤ መተተኛም ነበረ፤ መና ፍስት ጠሪዎችንና ጠንቋዮችን ሰበሰበ፤ ያስቈጣውም ዘንድ በእ ግዚአብሔር ፊት እጅግ ክፉ ነገ ርን አደረገ::

፲፮. እግዚአብሔርም ለዳዊትና ለልጁ ለሰሎሞን በዚህ ቤትና ከእ ስራኤል ነገድ ሁሉ በመረጥኋት በኢየሩሳሌም ስሜን ለዘለዓለም አኖራለሁ ባለበት በእግዚአብሔር ቤት ውስጥ የሠራውን ጣዖትና የተቀረጸውን ምስል አቆመ ::

፲፯. ያዘዝኋቸውንም ሁሉ በሙሴ ቃል የተሰጠውን ሕግና ሥርዐት ፍርድንም ሁሉ ቢያደርጉ ቢጠብቁም ለአባቶቻቸው ከሰጠ ኋት ምድር የእስራኤልን እግር እንደገና አላርቅም ::

፲፰.ምናሴም እግዚአብሔር ከእ ስራኤል ልጆች ፊት ከጣላቸው ከአሕዛብ ይልቅ ክፉ ይሠሩ ዘንድ በይሁዳና በኢየሩሳሌም የሚኖሩትን አሳተ::

፲፱. ወተናገሮ እግዚአብሔር ለም ናሴ ወለሕዝበ ዚአሁ፤ ወኢያ ጽምዕዎ::

፳. ወአምጽአ እግዚአብሔር ላዕሌሆሙ መላእክተ ኀይል ዘንጉሠ አሶራውያን፤ ወአኀዝዎ ለምናሴ ወሞቅሕዎ በመዋቅሕተ ሐፂን፤ ወነሥእዎ ብሔረ ባቢ ሎን ::

፳፩. ወሶበ ተመንደበ ኀሠሠ ገጸ እግዚአብሔር አምላኩ ወኀ ሥረ ፈድፋደ በቅድመ ገጸ እግዚ አብሔር አምላከ አበዊሁ::

፳፪. ወጸለየ ምናሴ ወልደ ሕዝቅ ያስ ንጉሥ ወይቤ ከመዝ::

፳፫. እግዚኦ አኃዜ ኵሉ ዓለም አምላኮሙ ለአበዊነ ለአብርሃም ወለይስሐቅ ወለያዕቆብ ወለ ኵሉ ፍሬሆሙ ለጻድቃን፣ ዘገበርከ ሰማየ ወምድረ ምስለ ኵሉ ዓለሞሙ፣

፳፬. ዘገሠጽካ ለባሕር በቃለ ትእዛዝከ፣ ዘዐጸከ ቀላያተ ወኀተ ምከ ግሩመ::

፲፱. እግዚአብሔርም ምናሴንና ሕዝቡን ተናገራቸው፤ ግን አል ሰሙትም::

፳. ስለዚህም እግዚአብሔር የአ ሶርን ንጉሥ ሠራዊት አለቆች አመጣባቸው፤ ምናሴንም በዛን ጀር ያዙት በሰንሰለትም አሥ ረው ወደ ባቢሎን ወሰዱት::

፳፩. በተጨነቀም ጊዜ አምላኩን እግዚአብሔርን ፈለገ፤ በአባቶ ቹም አምላክ ፊት ሰውነቱን እጅግ አዋረደ ::

፳፪. የንጉሡ የሕዝቅያስ ልጅ ምናሴም ጸለየ፤ እንዲህም አለ::

፳፫. ዓለምን ሁሉ የምትገዛ የአ ባቶቻችን የአብርሃም የይስሐቅ የያዕቆብም የጻድቃን ልጆቻቸ ውም አምላክ ሆይ! ሰማይና ምድርን ከዓለሞቻቸው ጋር የፈጠርህ፣

፳፬. በቃልህ ትእዛዝ ባሕርን የገ ሠፅሃት፣ ቀላዮችን(ጥልቆችን) የዘ ጋህ የሚያስፈራውንም የወሰ ንህ፣



፳፭.ውእቱኒ በስቡሕ ስምከ ዘኵሉ ይርዕድ፣ ወያድለቀልቅ እምቅድመ ገጸ ኀይልከ፣

፳፮. እስመ አልቦ ጽንፍ ለዕበየ ስብሐቲከ ግሩም መቅሠፍተ መዓ ትከ ላዕለ ኃጥኣን ::

፳፯. አልቦ ኍልቍ፤ ወአልቦ መስ ፈርት ለሣህለ ትእዛዝከ፤ እስመ አንተ እግዚአብሔር ባሕቲትከ ልዑል፣ መሐሪ ርኁቀ መዓት፣ ወብዙኀ ሣህል፣ ወመስተመይጥ ላዕለ ጌጋዮሙ ለዕጓለ እመሕ ያው::

፳፰. ይእዜኒ እግዚኦ አምላኮሙ ለጻድቃን እስመ አኮ ለጻድቅ ዘገበርኮ ለንስሐ፣ አኮ ለአብርሃም ወለይስሐቅ ወለያዕቆብ እለ ኢአ በሱ ለከ ፤ አላ ተመየጥ ንስሓ ዚአየ ለኃጥእ::

፳፱. እስመ አበስኩ እምኍልቈ ኆፃ ባሕር፤ ወብዙኅ ኃጢአትየ፤ አኮ ድልወት ሊተ አንቃዕዶ ወእ ርአይ ኑኖ ለሰማይ እምብዝኀ ጌጋይየ ሰራሕኩ በመዋቅሕተ ሐፂን ከመ እስሐታ ለነፍስየ እምኀጢ አትየ፣ ወበዝየኒ ኢተሥሕትኩ::

፳፭. ይኸውም በተመሰገነው ስምህ ነው፤ኀይልህ ከመገለጡ የተነሣ ሁሉ የሚርድና የሚንቀጠቀጥ፣

፳፮. ለክብርህ ከፍተኛነት ፍጻሜ የለውምና የቍጣህም መቅሠፍት በኃጥአን ላይ ግሩም ነው::

፳፯. በትእዛዝህ ለሚሆነው ይቅ ርታህ ስፍር፣ ቍጥር የለውም፤ ገናና እግዚአብሔር አንተ ብቻ ነህና፣ ይቅር ባይ፣ ከቍጣ፣ የራቅህ ይቅርታህ የበዛ፣ የሰው ንም ኀጢአት የምታስተሠርይ አንተ ነህ ::

፳፰. አሁንም አቤቱ የጻድቃን አምላካቸው አንተ ነህ፤ ንስሐን የፈጠርህ፣ ለጻድቅ ሰው አይደለ ምና፣ አንተን ላልበደሉ ለአብር ሃምና ለይስሐቅ፣ ለያዕቆብም አይደለምና፣ ነገር ግን የእኔን የኃጥኡን ንስሓ ወደማየት ተመ ለስ ::

፳፱. ቍጥሩ ከባሕር አሸዋ የሚበ ልጥ በደልን በድያለሁ፤ ኀጢኣ ቴም ብዙ ነውና፣ ከበደሌም ብዛት የተነሣ ቀና ብዬ የሰማ ይን ርዝመት አይ ዘንድ አገባቤ አይደለም፣ ሰውነቴን ከኀጢአቴ አሳር ፋት ዘንድ በብረት ቀፎ ደከምሁ በዚ ህም ደግሞ አላረፍሁም ::

፳፰. ኩኑኬ ፩ደ ሥጋ ወ፩ደ መን
ፈስ[፲፭] ወ፩ደ አሚነ በከመ ጸገ
ወክሙ እግዚአብሔር በርትዕ::

፳፱. ዲያቆን ይንግሮ ለኤጲስ ቆጶስ
ኵሎ ዘኮነ በከመ ክርስቶስ አልቦ
፩ዱ ዘገብረ ወኢምንትኒ ዘእንበለ
በአብ እስመ ፩ዱ ሥምረት ዘአብ
ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ::

፴. ወእምከመ ነሥአ ዲያቆን
ሢመተ እምኀበ ኤጲስ ቆጶስ
ይኩን እዝነ፣ ወዐይነ ወአፈ
ለኤጲስ ቆጶስ ወይንግሮ ትካዞሙ
ለሕዝብ በከመ ይደሉ በከመ ነገሮ
ዮቶር ለሙሴ ነቢይ ወተወክፈ
ቃሎ::[፲፮] ወዝንቱ ክብር ይደሉ
ለሕዝበ ክርስቲያን::

፴፩. ኢይፍታሕ ሕዝባዊ ወኢመ
ላሕቅት ዘእንበለ ዳእሙ ሥዩማን
ዘቤተ ክርስቲያን፣ እስመ ሰይጣን
ያመጽእ መሣግረ ለአግብርተ እግ
ዚአብሔር በኀበ ዕልዋን፣ ወይሜ
ህሮሙ ፅእለተ ወፅርፈተ፤ አልቦኑ
እምውስቴትነ ጠቢብ ዘይክል
ፈቲሐ ማዕከሌነ በርትዕ::[፲፯]

፴፪. ኢታብሕዎሙኬ ለአሕዛብ
ያእምሩ ምሥጢረ ኅቡአቲክሙ፤

፳፰. እግዚአብሔር በእውነት እን
ደሰጣችሁ አንድ አካል፣ አንድ
ልብ አንድ እምነት ይኑራችሁ::

፳፱. የአብ የወልድ የመንፈስ ቅዱስ
ፈቃድ አንድ ስለሆነ ክርስቶስ
ያለ አብ ምንም ምን የሠራው
አንድ ሥራ እንደሌለ ዲያቆኑ ለኤ
ጲስ ቆጶሱ የሆነውን ይንገረው::

፴. ዲያቆኑም ከኤጲስ ቆጶሱ ሹመ
ቱን ከተቀበለ በኋላ ለኤጲስ ቆጶሱ
እንደ ጆሮ እንደ ዐይንና እንደ አፍ
ይሁነው፤ ዮቶርም ለነቢዩ ለሙሴ
እንደነገረው ቃሉንም እንደተቀበ
ለው የሕዝቡን ችግራቸውን እንደ
ሚገባ ይንገርላቸው፤ ይህ ክብር
ለክርስቲያን ወገኖች ይገባል::

፴፩. ከቤተ ክርስቲያን ሹሞች
በቀር ሕዝባዊ አይፍረድ፣ ሽማግ
ሌዎችም አይፍረዱ፣ ሰይጣን ለእ
ግዚአብሔር አገልጋዮች በወንጀለ
ኞች ዘንድ አሽከላን ያማጣባቸዋ
ልና፣ ስድብንና ፅርፈትንም ያስተ
ምራቸዋልና፣ በመካከላችን በእው
ነት መፍረድ የሚችል ብልህ ከውስ
ጣችን የለምን::

፴፪.ምሥጢራችሁን ያውቁ ዘንድ
ለአሕዛብ አትፍቀዱላቸው፤ በእና

[፲፭] ኤፌ ፬ ፡ ፬
[፲፮] ዘፀ ፲፰ ፳፩ – ፳፪
[፲፯] ፩. ቆሮ ፮ ፡ ፫



ወኢትኑሥኡ፡ ስምዐ፡ እለ ኢየአ
ምኑ ላዕሌክሙ፤ አላ ዕቀቡ ዘተጸ
ገውክሙ እስመ ይቤ ሀቡ ዘነጋሢ
ለነጋሢ፣ ወዘእግዚአብሔር ለእግ
ዚአብሔር ::[፲፰]

፴፫. ወባሕቱ እመሰ ብከ ዕዳ ዘት
ፈዲ ኢታጕንዲ ውሂበ እንዘ
ትብል ለእጕየ ምእመን እፈድዮ፤
ወለዘኢየአምንሰ ኢይፈድዮ ወባ
ሕቱ ግበር በከመ ወሀበ እግዚእነ
ጸባሕተ ::

፴፬. ወአንትሙሰ አግብርተ እግ
ዚአብሔር ዕቀቡ ትእዛዛቲሁ ለክ
ርስቶስ፣ ወእመሰ ርኢክሙ ማዕ
ከለ አኀው ጋዕዘ ወተስናነ ርቱዕ
ትንግርዎሙ ለሥዩማን በእንቲ
አሆሙ፤ እመኒ እኩያነ ልማድ ወገ
ባርያነ ሀከክ ወጸላእያነ ሠናይ ወኢ
የሐውሩ በፍኖተ ርትዕ፣ ወለእለ
ከመዝ ገሥፅዎሙ ወአስተኀፍር
ዎሙ::

፴፭. ወእምከመሰ ነስሑ ተወከፍ
ዎሙ፤ ወእምከመ ገበርክሙ ከመዝ
ረሰይክሙ ሰላመ ማዕከለ አኀው
ወአድኀንክምዎሙ እምኀጢአት::

፴፮. መፍትውኬ ትሥረዩ ወትኅ
ድጉ አበሳ ለቢጽክሙ፣እስመ አዘዞ
እግዚአብሔር ለጴጥሮስ ሶበ ይቤሎ
እመሰ አበሰ ሊተ ቢጽየ ሚመጠነ

ንተም ላይ ያላመኑትን ሰዎች
ምስክርነት አትቀበሉ፤ የተሰጣች
ሁትን ጠብቁ እንጂ፣ የንጉሥን
ለንጉሥ፣ የእግዚአብሔርንም ለእ
ግዚአብሔር ስጡ ብሏልና::

፴፫. ነገር ግን የምትከፍለው ዕዳ
ቢኖርብህ ጌታችን ግብርን እንደ
ሰጠ አድርግ እንጂ፣ ለአማኙ ወን
ድሜ እከፍለዋለሁ ለማያምነው
ግን አልከፍለውም እያልህ መስጠ
ትን አታቌይ::

፴፬. የእግዚአብሔር አገልጋዮች
እናንተስ የክርስቶስን ትእዛዞች
ጠብቁ፤ በወንድሞቻችሁ መካከል
ጸብንና ክርክርን ብትሰሙ ስለ
እነርሱ ለሹሞቹ ትነግሯቸው
ዘንድ ይገባል፤ ልማዳቸው የክፉ
ክርክርን የሚያደርጉ በጎ ነገርንም
የሚጠሉ በቅንነት መንገድ የማይ
ሄዱ ቢሆኑም እንደ እነዚህ ያሉ
ትን ሰዎች ገሥጿቸው፤ አሳፍሯ
ቸውም::

፴፭. ንስሓ ከገቡ ግን ተቀበሏቸው፤
እንደዚህ ካደረጋችሁም በወንድሞ
ቻችሁ መካከል ሰላምን አደረጋችሁ፤
ከኀጢአትም አዳናቸኋቸው ::

፴፮. ለባልንጀሮቻችሁም በደላቸ
ውን ይቅር ብላችሁ ኀጢአታቸ
ውን ታስተሠርዩላቸው ዘንድ ይገ
ባል፣ ባልንጀራዬ ቢበድለኝ ምን

እኅድግ ሎቱ ስብዐኑ ወይቤሎ እግዚእነ ኢየሱስ ኢይብለከ ስብዐ አላ ዓዲ ስብዐ በበስብዕ ::[16]

፸፯. ከመዝኬ ይፈቅድ እግዚአብሔር ይግበሩ አርዳኢሁ፤ ወግሙራ ኢያኅድሩ ቂመ ወመዓተ ውስተ ልቦሙ ወኢፍትወተ እኩየ::

፸፰. አላ ባሕቱ ይግበሩ ሰላመ ማዕከሌሆሙ ከመ ይሕየዉ በ፩ ልብ እስመ ይቤ እግዚእነ ብፁዓን ገባርያነ ሰላም እስመ እሙንቱ ውሉደ እግዚአብሔር ይሰመዩ::

፸፱. ኢመፍትውኬ በሰንበተ ክርስቲያን ትግበሩ ቅስተ አላ ዳዕሙ ሰላመ ወፍትሕሰ ይኩን በባዕዳን መዋዕል::

፹. ወአንትሙሰ ኤጲስ ቆጶሳት ርቱዕ ይንበሩ ምስሌክሙ ካህናት ወዲያቆናት በውስተ ፍትሕ ወኢትፍትሑ በአድልዎ ወነሢአ ገጽ፣ አላ ፍትሑ በጽድቅ ወበርትዕ ከመ አግብርተ እግዚአብሔር::

፹፩. ወእመቦ ዘቦ ተስናን ምስለ ካልኡ ይምጽኡ ክልኤሆሙ ኅቡረ

ያህል ጊዜ ይቅር ልበለው ሰባት ጊዜ ነውን፣ ባለው ጊዜ ጌታችን ኢየሱስ ሰባ ጊዜ ሰባት ነው እንጂ ሰባት ጊዜ አይደለም ብሎ እግዚአብሔር ጴጥሮስን አዝዞታልና::

፸፯. እግዚአብሔር ደቀ መዛሙርቱ እንደዚህ ያደርጉ ዘንድ ይወዳል፣ ቂምንና ቁጣን ክፉ ምኞትንም ፈጽመው በልባቸው እንዳያሳድሩ ይወዳል::

፸፰. ነገር ግን በእነርሱ መካከል ሰላምን ያድርጉ፣ ጌታችን እንዲህ ብሏልና፤ ሰላምን የሚያደርጉ ብፁዓን ናቸው፤ እነእርሱ የእግዚአብሔር ልጆች ይባላሉና::

፸፱. በክርስቲያኖች ሰንበት ሰላምን ብቻ ነው እንጂ ክርክርን ታደርጉ ዘንድ አይገባም፣ ፍርድ ግን በሌሎች ቀኖች ይሁን::

፹. እናንተ ኤጲስ ቆጶሳት ግን በፍርድ ጊዜ ካህናትና ዲያቆናት ከእናንተ ጋራ ይቀመጡ ዘንድ ይገባል፤ በአድልዎና ፊት በማየት አትፍረዱ፤ ነገር ግን የእግዚአብሔር አገልጋዮች እንደመሆናችሁ በእውነትና በቅንነት ፍረዱ::

፹፩. ከወንድሙ ጋራ ክርክር ያለው ሰው ቢኖር ሁለቱም በአን

[16] ማቴ ፲፰ - ፳፩. ፳፪



ወይቁሙ ውስተ ዐውድ ወበከመ ጽሑፍ ውስተ ሕግ ፍትሑ እንከ ማዕከሌሆሙ በጽድቅ ወበርትዕ::

፹፪. ዐቀ ፍጡነ ወዕርቅዎሙ፤ ወግበሩ ሰላመ ማዕከሎሙ ዘእንበለ ይፃእ ፍትሕ እምኀበ ኤጲስ ቆጶስ ዲበ ዘአበሰ እስመ ሀሎ ምስሌክሙ ውስተ ዐውደ ፍትሕ ክርስቶስ ወልደ እግዚአብሔር::

፹፫. ወእመሰ ቦ ዘይቤ ዕገሌ ፀረፈ ላዕለ ስመ ክርስቶስ ወላዕለ እግዚአብሔር ወኢየሐውር በፍኖተ ርትዕ ኢትገሥሡዎ ፍትሐ ዘእንበለ ይቁም ካልኡ፣ ወእምከመ መጽኡ ኅቡረ ፍትሑ ማዕከሎሙ እስመ ፍትሕ ዘትወጽእ እምኔክሙ ትወስድ ውስተ ሕይወት፤ ወካዕበ ታወርድ ውስተ ኵነኔ ዘለዓለም እስመ ይቤ እግዚእነ ትልዉ ጽድቀ ወርትዐ::[17]

፹፬. ወለዘሰ ተዐውቀ ገሃደ አበሳሁ በርትዕ አቅምዎ፤ ወውእቱኬ ውጹእ እምሕይወት ዘለዓለም ወኢይሬእያ ለስብሐተ እግዚአብሔር ወይትኃፈር በኀበ ቅዱሳን፣ ወእመሰ ፈታሕክሙ በዐመፃ ትረክቡ ኵነኔ ወትትፈደዩ በከመ ምግ

ድነት መጥተው በአደባባይ ይቁሙ፤ በሕግ እንደተጻፈም በመካከላቸው በእውነትና በቅንነት ፍረዱ::

፹፪. ፈጥናችሁ ዐውቃችሁ አስታርቋቸው፤ በበደለው ላይ ከኤጲስ ቆጶሱ ዘንድ ፍርድ ሳይወጣ በመካከላቸው ሰላምን አድርጉ፣ በፍርድ አደባባይ የእግዚአብሔር ልጅ ኢየሱስ ክርስቶስ ከእናንተ ጋር አለና::

፹፫. ዕገሌ በክርስቶስ ስምና በእግዚአብሔር ላይ ተሳደበ የሚል ሰው ቢኖር በቅንነት መንገድ ባይሄድ ባላጋራው ሳይቆም ቸኩላችሁ አትፍረዱ፤ አንድነት ቢመጡ ግን በመካከላቸው ፍረዱ፤ ከእናንተ የምትወጣ ፍርድ ወደ ሕይወት ታደርሳለችና፤ ዳግመኛም ወደ ዘለዓለም ቅጣት ታወርዳለችና፤ ጌታችንም እውነትንና ቅንነትን ተከተሉ ብሏልና::

፹፬. በደሉ ተገልጦ የታወቀውን ግን በሚገባ ወስኑበት፤ እርሱም ከዘለዓለም ሕይወት የወጣ ነው፣ የእግዚአብሔርንም ክብር አያይም፣ በቅዱሳንም ዘንድ ያፍራል፤ በዐመፅ ብትፈርዱ ግን ቅጣትን ታገኛላችሁ፤ እግዚአብሔር በሰጠና

[17] ዳን ፲፫ ፵፯

ባረክሙ በከመ ፈደዮሙ እግዚአብ ሐር ለክልኤቱ ረበናት እለ ነበቡ ሐሰተ ላዕለ ሶስና፡፡[፲፯]

፻፳፭. ተዐቀቡኬ እምነቢበ ሐሰት እስመ ዘይነብብ ሐሰተ ብዙኀ ይት ኴነን ፡፡

፻፳፮. ኢትኩኑ ከመ ዕደው እለ ወጽኡ እምሕግ ወእለ ነበቡ ሐሰተ ላዕለ ናቡቴ በሰማርያ፡፡ [፲፰] ወበከመ ማኅበረ አይሁድ እለ ነበቡ ሐሰተ ላዕለ እግዚእነ በኢየሩሳሌም ወእለ ነበቡ ሐሰተ ላዕለ እስጢፋኖስ ቀዳሜ ሰማዕት፡፡[፲፱]

፻፳፯. መፍትውኬ ይኩኑ ስምዐ ዕደው የዋሃን እለ አልቦሙ መዓት ንጹሓን ወኄራን ወመፍ ቀርያነ ትሕትና ወምእመናን ወመ ምለክያነ እግዚአብሔር እለ አል ቦሙ እከይ፣ እስመ ይደሉ ስምዐ ንጹሓን እለ አልቦሙ ነውር ወዘ ጥዩቅ ስምዖሙ፡፡

ላይ ሐሰት የተናገሩትን ሁለቱን ረበናት ፍዳቸውን እንደከፈላቸው እንደ ሥራችሁ ፍዳችሁን ትቀበላ ላችሁ፡፡

፻፳፭. ሐሰትን ከመናገር ተጠበቁ፤ ሐሰትን የሚናገር ሰው በብዙ ይፈ ረድበታልና፡፡

፻፳፮. በመሰማርያ በናቡቴ ላይ ከሕግ ወጥተው ሐሰትን እንደ ተናገሩ ሰዎች አትሁኑ፣በኢየሩሳ ሌም በጌታችን ላይ ሐሰትን እንደ ተናገሩ እንደ አይሁድ ማኅበርም፣ በሰማዕታት መጀመሪያ በእስጢ ፋኖስም ላይ ሐሰትን እንደተናገሩ አትሁኑ፡፡

፻፳፯. የዋሆች፣ የማይቆጡ፣ ንጹ ሐን፣ ቸሮች፣ ትሕትናን የሚወ ድዱ ፣ የታመኑ፣ እግዚአብሔርን የሚያመልኩ ሰዎች፣ ምስክር ይሆኑ ዘንድ አግባብ ነው፤ ነውር የሌለባቸው ምስክርነታቸውም የተ ረጋገጠ፣ የንጹሐን ሰዎች ምስክር ነት ይገባልና፡፡

[፲፯] ዳን ፲፫. ፶፱-፷
[፲፰] ነገ ፩ ፳.፲
[፲፱] ግብ ሐዋ. ፯ ፲፩-፲፫



፻፳፰. ወለእለሰ የሐይዉ ከመዝ ኢትትወከፉ ስምዖሙ ወእመሂ ስምዖሙ ኀብረ ለብዙኃን ሰማዕተ ሐሰት በአሐቲ ምክር ኢትስምዑ ቃሎሙ እስመ ይቤ ኢትኅበር

ውስተ ማኅበሮሙ ዘደም ፣ ወዓዲ እዙዝ ውስተ ሕግ ወው ዴተ ሐሰት ኢትስጠው ወኢት ንበር ምስለ ዘይዔምፅ ከመ ኢት ኩን መዐምፅ ስምዐ ወኢትደመር ምስለ ብዙኃን ለዐምፆ፡፡ [፳]

፻፳፱. ወእመሰቦ ዘመጽአ ኀቤክሙ ውስተ ፍትሕ ሕቱ ሕይወቶ ዘከመ እፎ ውእቱ ግዕዙ ወል ማዱ፤ ወተረክቡ ሰማዕት በእንቲ አሁ ከመ አልቦ ጹግ አላ ዳእሙ የኀሥሥ ጽድቀ ወመፍቀሬ እግ ዚአብሔር ወተወካፌ ነግድ ወመ ፍቀሬ ነዳያን ወመፍቀሬ አኀው ዘኢያፈቅር ረባሐ ወኢመሣጢ ወኢሰካሪ፣ ወኢሐካይ መሐሪ ዘኢ ይሰፍሕ እዴሁ ውስተ ትዕግልት ወለዘከመዝ ግብሩ ፍትሑ ሎቱ በጽድቅ፡፡

፻፳፰. ነገር ግን እንደዚህ የሚኖሩ ትን ሰዎች ምስክርነታቸውን አት ቀበሉ፣ የብዙዎች የሐሰተኞች ምስክ ሮችምስክርነታቸው በአንዲት ምክር ቢ.ተባበር ቃላቸውን አት ስሙ፤ ደምን ከሚያፈሱ ማኅበር ጋራ አትተባበር ብሏልና፣ዳግ መኛም በኦሪት የሐሰት ነገር ሥራን አትቀበል ተብሎ ታዝዟል፤ ሐሰ ተኛ ምስክርም እንዳትሆን ከሚዋ ሽም ጋር አትኑር፤ ለአመፅም ከብዙዎች ጋራ አትጨመር፡፡

፻፳፱. ለፍርድ ወደ እናንተ የመጣ ሰው ቢኖር፣ ግብሩና ልማዱ እን ዴት እንደሆነ ሕይወቱን መርምሩ፣ ክፋት እንደሌለበት፤ ነገር ግን ጽድ ቅን የሚፈልግ እግዚአብሔርንም የሚወድ እንግዳ ተቀባይ ነዳያንን የሚወድ፣ ወንድሞችን የሚወድ፣ ገንዘብን የማይወድ፣ ነጣቂ፣ ሰካ ራም፣ ሰነፍ ያይደለ፣ የሚራራ፣ እጁን ወደቅሚያ የማይዘረጋ እን ደሆነ ምስክሮች ቢገኙ ሥራው እን ዲህ ለሆነ ሰው በእውነት ፍረዱ ለት፡፡

[፳] ዘፀ ፳፫ ፡ ፪

፲. ወለዘሰ ይነብብ ሐሰተ ላዕለ ቢጹ ገሥጽዎ እስመ ቀታሌ እኑሁ ውእቱ ከመ ርእዮሙ ካልአን ይፍርሁ ወኢይትልዉ ፍኖቶ::

፲፩. ወእመሰ ቦ ዘተዐውቀ አበሳሁ በውስተ ፍትሕ ገሥጽዎ ወአስተኃፍርዎ በከመ አቅድምነ ነጊረ::

፲፪. እመ ቦ ዘሰከየ ኢትፍትሑ ለ፪ሆሙ ዘእንበለ ዳእሙ የሀልዉ ክልኤሆሙ ኅቡረ ውስተ ዐውድ ወእመሰ ፈታሕክሙ ለ፩ በዐመፃ ዘእንበለ ይቁም ካልዑ ውስተ ዐውደ ፍትሕ ኮንክሙኬ ከመ ነባብያነ ሐሰት ወከመ ረበናት እለ ነበቡ ሐሰተ ላዕለ ሶስና በባቢሎን፤ ወእሙንቱሰ አውረድዋ ውስተ ፍትሐ ሞት ወባሕቱ ለሶስና አድኅና ዳንኤል ነቢይ፤ ወለእለሂ ሐሠዉ ላዕሌሃ አውረዶሙ ውስተ ኵነኔ ሞት::[፳፩]

፲፫. ወከማሁ አንትሙኒ ለእመ ኢፈታሕክሙ በጽድቅ ወበርትዕ ይመጽእ ላዕሌክሙ መቅሠፍተ መዓቱ ለእግዚአብሔር::

፲. ባልንጀራው ላይ ሐሰትን የሚናገረውን ግን፣ ሌሎች አይተው ይፈሩ ዘንድ ጐዳናውንም እንዳይከተሉ ገሥጹት፤ ወንድሙን ገዳይ ነውና::

፲፩.በደሉ የታወቀ ሰው ቢኖር አስቀድመን እንደተናገርን በፍርድ ጊዜ ገሥጻችሁ አሳፍሩት::

፲፪. የከሰሰ ሰው ቢኖር ሁለቱም በአንድነት በአደባባይ ሳይኖሩ ለአንዱ አትፍረዱ፤ ባላጋራው በአደባባይ ሳይቆም ለአንዱ በማድላት ብትፈርዱ ግን በሐሰት እንደሚፈርዱና በባቢሎን በሶስና ላይ ሐሰትን እንደተናሩ ረበናት ትሆናላችሁ፤ እነርሱ ወደሞት ፍርድ አውርደዋት ነበር፣ ነገር ግን ነቢዩ ዳንኤል ሶስናን አዳናት በእርሷ ላይ ሐሰት የተናገሩትንም ወደ ሞት ቅጣት አወረዳቸው::

፲፫. እንደዚሁም እናንተ በእውነትና በቅንነት ካልፈረዳችሁ የእግዚአብሔር የቍጣው መቅሠፍት በእናንተ ላይ ይመጣባችኋል::

[፳፩] ዳን ፲፫ ፶፬



፲፬. ወባሕቱ እመሰ ፈታሕክሙ በጽድቅ ወበርትዕ ትረክቡ ዐስበ ሠናየ ወሕይወተ ዘለዓለም::

፲፭. ዑቁኬ አኀው ፍቁራን ወግበሩ ሠናየ ኵሎ ጊዜ ከመ ትርከቡ ክብረ በኀበ እግዚአብሔር ምስለ አበው ቅዱሳን አብርሃም ይስሐቅ ወያዕቆብ በመንግሥተ ሰማያት ውስተ ሕይወት ዘለዓለም እስመ ርትዕ በኀበ እግዚአብሔር ውእቱ::

፲፮. ፍትሑ እንከ በጽድቅ ወበሰላም ዘእንበለ መዓት እስመ ዘያምእዕ ቢጾ በከንቱ ይከውን መክፈልተ ገሃነም እስመ ተብህለ ዘእንበለ ይዕርብ ፀሐይ አቊርሩ መዓተክሙ፤ወኢትሀብዎ ፍኖተ ለሰይጣን ዘይሰርቅኒ ኢይስርቅ:: [፳፪]

፲፯. ወካዕበ ይቤ ዳዊት ተምዑ ወኢተአብሱ[፳፫] ተፋቀሩኬ በበይናቲክሙ፤ ወአዕትቱ እከየ እምልብክሙ::

፲፬. በእውነትና በቅንነት ብትፈርዱ ግን በጎ ዋጋንና የዘለዓለም ሕይወትን ታገኛላችሁ::

፲፭. የተወደዳችሁ ወንድሞች ሆይ አስተውሉ፤ ከቅዱሳን አባቶች ከአብርሃም፣ ከይስሐቅና ከያዕቆብ ጋራም በመንግሥተ ሰማያት በዘለዓለም ሕይወት ከእግዚአብሔር ክብርን ታገኙ ዘንድ ሁልጊዜ በጎ ሥራን ሥሩ እውነት በእግዚአብሔር ዘንድ ነውና::

፲፮. እንግዲህ ያለቍጣ በእውነትና በሰላም ፍረዱ፣ ባልንጀራውን በከንቱ የሚያስቈጣ ሰው የገሃነም እድል ፈንታ ይሆናልና፣ ፀሐይ ሳይገባ ቍጣችሁን አርቁ፤ ለሰይጣንም መንገድን አትስጡት፣ የሚሰርቅም አይስረቅ ተብሏልና::

፲፯. ሁለተኛም ዳዊት ተቈጡ ግን አትበድሉ ብሏል፤ እርስ በርሳችሁ ተፋቀሩ፣ ከልባችሁም ክፋትን አስወግዱ::

[፳፪] ኤፌ ፬ ፡ ፳፮
[፳፫] መዝ ፬ ፡ ፬

፺፰. ስምዑ ዘይቤ በወንጌል መምህርነ ወእግዚእነ ወመድኀኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ ሶበ ታበውእ አምኃከ ውስተ ምሥዋዕ ወበህየ ተዘከርከ ከመቦ እኁከ ዘተኀየሰከ ኀድግ ህየ መባኣከ ቅድመ ምሥዋዕ ወሑር ቅድመ ተኳነን ምስለ እኁከ ወእምዝ ገቢአከ አብእ አምኃከ::[፳፩]

፺፱. ወመሥዋዕቱሰ ለእግዚአብሔር ልብ የዋህ ወመንፈስ ትሑት ፤ ጸሎት ወአኰቴት::

፻. ወእመሰ አምዐዕከ ቢጸከ ወአኅዘንከ ልቦ ኢይትዌከፍ እግዚአብሔር መሥዋዕተከ ወጸሎተከ::

፻፩. መፍትውኬ ለክሙ እ አኀው ፍቁራን ትጸልዩ ወትስአሉ ኵሎ ጊዜ ወትንግሩ ስእለተክሙ ኀበ እግዚአብሔር ከመ ያዕትት እምኔክሙ ኵሎ ቍጥዓ ወመዓተ ፤ ሰብሕዎ

፺፰. መምህራችን ፡ ጌታችንና መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በወንጌል ያለውን ስሙ ፤ መባህን ወደ መሠዊያው በምታቀርብ ጊዜ በዚያ የተጣላህ ወንድምህ እንዳለ ብታስብ መባህን በመሠዊያው ፊት ትተህ ሂድና አስቀድመህ ከወንድምህ ጋራ ታረቅ ፡ ከዚህ በኋላ ተመልሰህ መባህን አቅርብ::

፺፱. የእግዚአብሔርም መሥዋዕቱ ቅን ልብና ትሑት መንፈስ ጸሎትና ምስጋና ነው ::

፻. ወንድምህን ብታበሳጭ ፡ ልቡንም ብታሳዝን ግን እግዚአብሔር መሥዋዕትህንና ጸሎትህን አይቀበልህም::

፻፩. የተወደዳችሁ ወንድሞች ሆይ ፡ ቍጣንና መዓትን ሁሉ ከእናንተ ያርቅ ዘንድ ሁልጊዜ ትጸልዩና ትለምኑ ዘንድ ወደ እግዚአብሔርም ልመናችሁን ትነግሩ ዘንድ አግባብ ነው፤

[፳፩] ማቴ ፭ ፡ ፳፫ - ፳፬



ለእግዚአብሔር ወትረ በበጊዜሁ፤ ወተዘከሩ ስሞ ልዑለ ፤ ከመ ያሰስል እምላዕሌክሙ ጽልአ ወመዓተ ወቂመ ከመ ትክሀሉ ጸልዮ በልብ ንጹሕ ዘአልቦ ርስሐት፣ እስመ አዘዘነ እግዚአብሔር ናፍቅር ጸላእተነ ወኢ ንጽላእ አዕርክቲነ፤ ወካዕበ ይቤ ኢትጽላእ ኵሎ ሰብአ እም ውስቴቶሙ ገሥጽ ወእምውስቴቶሙ መሐር፤

፻፪. ወኢትጽልኦ ለእኁከ በምልዐ ልብከ ወኢትስማዕ ውዴተ በላዕሌሁ ፤ ወኢትትዐቀፍ በእንቲአሁ ወኢትስድዶ ለግዩር ዘይነብር ኀቤከ እስመ አንተኒ ግዩረ ኮንከ በምድረ ግብጽ ፤ ወኢትጽልኦ ለኤዶማዊ እስመ እኁከ ውእቱ::[፳፪]

፻፫. ወዳዊትኒ ይቤ ወእመኒ ፈደይክዎሙ ለእለ ይፈድዩኒ እኩየ ለያውድቁኒ ጸላእትየ ዕራቅየ::[፳፫]

እግዚአብሔርን ዘወትር በየጊዜው አመስግኑት ፤ ዕድፈት በሌለበት በንጹሕ ልብ መጸለይ እንድትችሉም ከእናንተ ጥላቻንና ቍጣን ቂምንም ያስወግድ ዘንድ ልዑል ስሙን ጥሩ ፣ እግዚአብሔር ጠላቶቻችንንም እንዳንጠላ አዝዞናልና ፣ ሁለተኛም ሰውን ሁሉ አትጥላ ፣ ከእነርሱ ውስጥ ያሉትን ገሥፅ፣ ከእነርሱም ውስጥ ላሉት ራሩ::

፻፪. ወንድምህን በሙሉ ልብህ አትጥላው ፤ ነገር ሥራንም በእርሱ ላይ አትስማ፣ በእርሱም ነገር አትሰነካከል፣ በአንተ ዘንድ የሚኖረውን መጻተኛም አታባርረው፤ አንተም በግብጽ አገር መጻተኛ ሆነህ ነበርና፤ የኤዶም ሰውንም አትጥላው፤ ወንድምህ ነውና ::

፻፫. ዳዊትም እንዲህ አለ፣ ለሚ መልሱልኝ ሰዎች ክፉን መልሼ ላቸው እንደሆነ ጠላቶቼ ራቁቴን ይጣሉኝ፤

[፳፪] ዘዳግ ፳፫ ፡ ፯
[፳፫] መዝ ፯ ፡ ፬

## አንቀጽ ፲ወ፩

በእንተ ከመ መፍትው ለክርስ ቲያን ይኅድጉ ወትረ አበሳ ለቢጾሙ፣ ወኢያንብሩ ውስተ ልቦሙ ቂመ ፣ ወኢየኀልዩ እከየ::

፩. ወእመሰ ትፈቅዱ ትኩኑ ክርስቲያነ ጥዩቀ ሑሩ በፍኖተ እግዚአብሔር ወፍትሑ ኵሎ ማእሠረ ኃጢአት[፩] ፤ እስመ አዘዘክሙ መድኅን ትኅድጉ አበሳ ለቢጽክሙ ስብዐ በበስ ብዕ ::[፪]

፪. ወእመሰ ኢትፈቅዱ ትሥ ረዩ ሎሙ ስምዑ ዘይቤ ኤር ምያስ ነቢይ ወአንተሰ ሶበ ኀለይከ በልብከ እከየ፣ወዐቀብከ ጽልአ ወፈታሕከ በመዓት ኢት ክል ዐሪገ ጸሎትከ ኀበ እግዚ አብሔር፣ እስመ ኢገበርከ ትእ ዛዛቲሁ ለእግዚእከ ::[፫]

፫.ወእመ ኅደገ አበሳሁ ለእኁከ ፸ተ ፯ተ ወ፺ ጊዜ ኮንከ ሕፁፀ መዓት ወብዙኀ ምሕረት

፩ ኢሳ. ፶፰ - ፯
፪ ማቴ. ፲፰ ፡ ፳፩ -፳፪
፫ ዘካር. ፰ ፡ ፲፯

## አሥራ አንደኛ አንቀጽ

ክርስቲያኖች ዘወትር የወንድ ሞቻቸውን በደል ይቅር ይሉ ዘንድ ፤ በልቦናቸውም ቂምን እንዳያኖሩ ፤ ክፋትንም እንዳ ያስቡ እንደሚገባ ይናገራል።

፩. ፍጹማችሁ ክርስቲያንን ትሆኑ ዘንድ ብትወዱ ግን በእ ግዚአብሔር መንገድ ሂዱ ፤ የኀ ጢአት ማሠሪያንም ሁሉ ፍቱ፣ መድኀኔ ዓለም ሰባ ጊዜ ሰባት ይቅር ትሉ ዘንድ አዝዟችኋልና::

፪. ይቅር ትሏቸው ዘንድ ባት ወዱ ግን ነቢዩ ኤርምያስ የተና ገረውን ስሙ አንተ ፣ በልቡናህ ክፋትን ብታስብ ፤ ጠብንም ብትጠባበቅ ፤ በቍጣም ብትፈ ርድ ጸሎትህ ወደ እግዚአብሔር ማረግ አትችልም ፤ የጌታህን ትእዛዝ አልሰራህምና ::

፫. የወንድምህን በደል አራት መቶ ዘጠና ጊዜ ይቅር ብትል ግን ራስህን ታድን ዘንድ



ከመ ታድኅን ርእሰከ ፤ ወእመሰ ገበርከ ከመዝ ትከውን ወልደ ለአቡከ ዘበሰማያት ወሶበ ሰአልከ ኀቤሁ ይሰምዐከ ጸሎተከ ከመ ዐርከ ምእመን::

፬. ወበእንተዝ ኤጲስ ቆጶሳት ሶበ ተጋባእክሙ ለጸሎት ወለስብሐት ወለቅኔ ፣ ወለአ ንብቦ ቃለ ተግሣጽ አንብቡ ቃለ መጻሕፍት ቅዱሳት::

፭. ወይቁም ዲያቆን ማዕከሌ ክሙ እንዘ ይጸርሕ በዐቢይ ቃል ወይብል እመ ቦ ዘቦ ውስተ ልቡ ቂም ወቅንአት ወጕሕሉት ወኵሉ እኩይ ላዕለ ቢጹ ፍጡነ ይትዐረቅ ምስ ሌሁ፣ ወእምዝ ይትዌከፍ እግዚአብሔር ጸሎቶሙ ወስእለ ቶሙ ::

፮. ወሶበ ትበውኡ ከመዝ በሉ፤ ሰላመ እግዚአብሔር የሀሉ ውስተ ዝንቱ ቤት፤ ወእመቦ ሀየ ወልደ ሰላም ያዕርፍ ሰላምክሙ ላዕሌሁ::[፬] በከመ ጽሑፍ ሰላም ውእቱ ለርኁቃን ወለቅሩባን ሕዝብ እለ የአምኑ በክርስቶስ::[፭]

፬ ማቴ.፲ - ፲፪
፭ ኤፌ. ፪ - ፲፯

ቸርነትህ የበዛ ቍጣህም ያነሰ ሆንህ ፤ እንዲህም ብታደርግ የሰማያዊ አባትህ ልጅ ትሆና ለህ፤ ወደ እርሱም በለመንህ ጊዜ እንደታመነ ባልንጀራ ጸሎ ትህን ይሰማሃል፣

፬. ስለዚህም ኤጲስ ቆጶሳት ሆይ ለጸሎትና ለምስጋና፣ ለአገልግ ሎት የተግሣፅን ቃልም ለማ ንበብ በተሰበሰባችሁ ጊዜ ቅዱ ሳት መጻሕፍትን አንብቡ::

፭. ዲያቆኑም በታላቅ ድምፅ አሰምቶ እየተናገረና እንዲህ እያለ በመካከላቸው ይቁም፤ በባ ልንጀራው ላይ በልቡ ቂምና ቅናት፤ ክዳትና ክፋት ሁሉ ያለው ቢኖር ከእርሱ ጋር ፈጥኖ ይታረቅ ፣ ከዚህ በኋላ እግዚአ ብሔር ልመናቸውንና ጸሎታ ቸውን ይቀበላል::

፮. ወደ ቤትም በምትገቡ ጊዜ እንዲህ በሉ ፤ በዚህ ቤት የእግ ዚአብሔር ሰላም ይደር በሉ ፤ በዚያም የሰላም ልጅ ቢኖር በክ ርስቶስ ላመኑ ሰዎች ለራቁ ትም ፤ ለቀረቡትም ሕዝቦች ሰላም ነው ተብሎ እንደተጻፈ፣ ሰላማችሁ በእርሱ ይደር::

፯. መፍትው ኵሎሙ እለ ይበውኡ ውስተ ቤተ ክርስቲያኑ ለእግዚአብሔር ይስአሉ ኀቤሁ ከመ ይፌኑ ሰላመ ላዕለ ሕዝቡ::

፰. መፍትው ኤጲስ ቆጶሳት ይኩኑ ገባርያነ ሰላም፣ ወመሐርያነ እለ ይሠርዩ ለዘአበሰ ላዕሌሆሙ፤ ወይትዌከፉ ንስሐሆሙ ለእለ ይትመየጡ ኀበ እግዚአብሔር::

፱. ወእመሰ ኢገብሩ ከመዝ ኢይሰመዩ ኤጲስ ቆጶሳተ፣ አላ ዳእሙ ይሰመዩ አቢቦሎሳውያን እኩያነ::

፲. ወእመሰ ይጼሊ ኤጲስ ቆጶስ ሰላመ በእንተ ባዕዳን እፎኬ እንከ ለሊሁ ኢይከውን ሰላማዌ ከመ ኢይኩን ወልደ ጽልመት ወይሰመይ ወልደ ብርሃን::

፲፩. ወእመሰ ለሊሁ አልቦ ሰላም እፎ ይክል ውሂበ ለካልኣን::

፯.ወደ እግዚአብሔር ቤተ ክርስቲያን የሚገቡ ሁሉም በሕዝቡ ላይ ሰላምን እንዲልክ ወደ እርሱ ይለምኑ ዘንድ አግባብ ነው::

፰. ኤጲስ ቆጶሳት ሰላምን የሚያደርጉ፣ እነርሱንም የበደሏቸውን ይቅር የሚሉ፤ ርኅሩኃን ወደ እግዚአብሔር የሚመለሱትንም ንስሐቸውን የሚቀበሉ ይሆኑ ዘንድ አግባብ ነው::

፱. እንደዚህ ባያደርጉ ግን ኤጲስ ቆጶሳት አይባሉም ፣ ነገር ግን ክፉዎችን አቢቦሎሳውያን ይባላሉ እንጂ ::

፲.ኤጲስ ቆጶሱ ስለ ባዕዳን ሰላምን ከጸለየ እርሱ ራሱ የጨለማ ልጅ እንዳይሆን የብርሃን ልጅ ይባል ዘንድ እንዴት ሰላማዊ አይሆን?

፲፩. እርሱ ሰላም የሌለው ከሆነ ግን ለሌሎች ሰላምን መስጠት እንዴት ይችላል?



፲፪. ወበእንተዝ መፍትው ቀዳሜ ኵሉ ትግባእ ሰላም ይኩን ዘእንበለ እከይ ወጽልእ አላ ባሕቱ በፍቅር ወበሰላም ይርዐዮሙ ለአባግዐ ክርስቶስ፤ ወፈድፋደሰ ይዕቀቦሙ ከመ ዐርክ ምእመን ወይድኅኑ ኅቡረ ወይከውኑ ፩ደ መርዔተ::

፲፫. ወእኩያንሰ እለ ይገብሩ ዐመፃ ወጽልአ ወሀከከ ይከውኑ ርኁቃነ እምእግዚአብሔር ፣ እስመ እግዚአብሔር አምላከ ምሕረት ይፈቅድ ያስተጋብኦሙ ለኵሎሙ ትውልድ ውስተ ንስሐ በትምህርተ መንፈስ ቅዱስ ወጻድቃን ወነቢያት መሀሮሙ ለእለ እምቅድመ አይኅ ነበሩ አሕዛብ በትምህርተ አቤል፣ወበተግሣፀ አቤል ወሴት፣ ወሄኖስ ወኄኖክ ዘዐርገ ውስተ ሰማይ ወለእለሰ እምድኅረ አይኅ መሀሮሙ በኖኅ ፤ ወለእለሂ በሰዶም በቃለ ሎጥ መፍቀሬ ነግድ፤ ወእምድኅረ ሎጥ በነገረ መልከ ጼዴቅ ወአበው ቀደምት ወኢዮብ መፍቀሬ እግዚአብሔር ::

፲፪. ስለዚህም ከሥራ ሁሉ አስቀድሞ ያለ ክፋትና ጠብ ሰላም ይሆን ዘንድ አግባብ ነው ፤ ነገር ግን የክርስቶስን በጎች በፍቅርና በሰላም ፈጽሞ ይጠብቃቸው ፣ ይልቁንም እንደታመነ ወዳጅ ይጠብቃቸው፣ እነርሱም በአንድነት ይድናሉ ፣ አንድ መንጋም ይሆናሉ::

፲፫. ዐመፅን ጥላቻንና ክርክርን የሚያደርጉ ክፉዎች ግን ከእግዚአብሔር የተለዩ ይሆናሉ ፣ የምሕረት አምላክ እግዚአብሔር በመንፈስ ቅዱስ ትምህርት በጻድቃን በነቢያት ፍጥረቱን ሁሉ ወደ ንስሐ ይመልሳቸው ዘንድ ይወዳልና ፣ ከማየ አይኅ አስቀድመው የነበሩትን በአቤልና ሴት ፣ በሄኖስና ወደ ሰማይ ባረገው በኄኖክ ትምህርትና ተግሣጽ አስተማራቸው ፤ ከማየ አይኅ በኋላ የነበሩትን ግን በኖኅ አስተማራቸው ፤ በሰዶም የነበሩትንም እንግዳን በሚወድ በሎጥ ቃል ፣ ከሎጥም በኋላ የነበሩትን በመልከ ጼዴቅ ፣ በቀደምት አበውና እግዚአብሔርን በሚወድ በኢዮብ ቃል አስተማራቸው::

፲፬. ወለግብጻውያንሰ ወደቂቀ እስራኤል በትእዛዘ ሙሴ ወኢያሱ ወልደ ነዌ ወካሌብ ወፊንሐስ ወእለ እምድኅሬሆሙ::

፲፭. ወእምድኅረ ሕግሰ በተግሣጸ መላእክት ወነቢያት፣ ወእምድኅረ እሉ ኵሎሙ እግዚእነ ዘተሠገወ ወተሰብአ እምእግዝእትነ ቅድስት ድንግል ማርያም እምድኅረ ተወድየ ዮሐንስ ውስተ ቤተ ሞቅሕ ሰበከ እንዘ ይብል ነስሑ እስመ ቀርበት መንግሥተ ሰማያት::[፯]

፲፮. ወእምድኅረ ሐመ በዲበ ዕፀ መስቀል አዘዘነ ለነ ለ፲ ወ፪ቱ ሐዋርያቲሁ ንስብክ ምስለ ጌር እኁነ ጳውሎስ፤ንሕነ እሙንቱ ዘጸገወነ ንኩን ስምዐ በእንተ ወልዱ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ::

፲፯. ወዓዲ ምስሌነ ያዕቆብ እኁሁ ለእግዚእነ ፣ ወ፯ቱ ዲያቆናት ፤ ሰማዕነ እምአፉሁ ለእግዚእነ ቃለ ሕይወት፤ ወአመነ ኵልነ ወአእመርነ ከመ ውእቱ ኢየሱስ ክርስቶስ ሥምረቱ ለእግዚአብሔር አብ::

፯ ማቴ ፬ ፡ ፪

፲፬. ግብጻውያንንና የእስራኤልን ልጆች ግን በሙሴና በነዌ ልጅ በኢያሱ ፣ በካሌብና በፊንሐስ ፣ ከእነርሱ ቀጥለውም በነበሩት ትእዛዝ አስተማራቸው::

፲፭. ከሕግ በኋላ ግን በካህናት በነቢያት ምክር አስተማራቸው፣ ከእነዚህ ሁሉ በኋላም ከቅድስት ድንግል ከእመቤታችን ማርያም ፈጽሞ ሰው የሆነው ጌታችን ዮሐንስ ወደ ግዞት ቤት ከገባ በኋላ መንግሥተ ሰማያት ቀርባለችና ንስሐ ግቡ እያለ አስተማራቸው::

፲፮. በዕፀ መስቀል ላይ መከራ ከተቀበለ በኋላም ቸር ከሚሆን ከወንድማችን ከጳውሎስ ጋር እናስተምር ዘንድ እኛን ዐሥራ ሁለቱን ሐዋርያት አዘዘን፣ ስለ ልጁ ስለ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ምስክር እንሆን ዘንድ ጸጋን የሰጠን እኛ ነን::

፲፯. ደግመኛም ከእኛ ጋራ የጌታችን ወንድም ያዕቆብ ነበር ፤ ሰባቱ ዲያቆናትም ነበሩ፤ ከጌታችን አንደበት የሕይወት ቃልን ሰምተን ሁላችን አምነናል ፤ ኢየሱስ ክርስቶስም የእግዚአብሔር አብ ፈቃዱ እንደሆነ አውቀናል ::



፲፰. ንዜንወክሙ ፍጹመ በኀቤሁ ከመ ኢይማስን ኵሉ ዘየአምን ቦቱ ወናዕርግ ሎቱ ስብሐተ በአሐቲ ቃል ከመ ንርከብ ሕይወተ ዘለዓለም::

፲፱. ወከመዝ አዘዘነ እግዚእነ ንጸሊ ኀበ አብ እንዘ ንብል ይኩን ፈቃድከ በከመ በሰማይ ከማሁ በምድር::[፰]

፳. ወበከመ ይሴብሕዎ ኀይላት ሰማያውያን ወመንፈሳውያን ከማሁ ይሴብሕዎ ለአሐዱ እግዚአብሔር ኵሉ ፍጥረት በዲበ ምድር ፤ ወለዋሕድ ወልዱ እግዚእነ ወአምላክነ ወመድኀኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ::

፳፩. ዝ ውእቱ ሥምረቱ ለክርስቶስ ከመ ይብዝኁ እለ ይድኅኑ ወኢይማስን ወኢ፩ዱ እምኔሆሙ ወኢትሕፀፅ ቤተ ክርስቲያን ዝኬ ውእቱ ሥምረቱ ከመ ንሰብሖ ወንወድሶ በ፩ዱ ሕሊና ወንስግድ ሎቱ በ፩ዱ መንፈስ::

፳፪. ኢትቅትሉ ነፍሰ እንተ ሐይወት በንስሐ ወድኅነት በቍጥዓ ወበመዓት::

፰ ማቴ ፮ ፡ ፱ - ፲

፲፰. ያመነበት ሁሉ በእርሱ ዘንድ እንዳይጠፋ ፈጽመን እንነግራችኋለን ፤ የዘለዓለም ሕይወትንም እናገኝ ዘንድ በአንዲት ቃል ምስጋናን እናቅርብለት ::

፲፱. እንደዚሁም ፈቃድህ በሰማይ እንደሆነ እንዲሁ በምድር ይሁን እያልን እንድንጸልይ ጌታችን አዘዘን ::

፳. ሰማያውያንና ረቂቃን መላእክት እንደሚያመሰግኑት እንዲሁም በምድር ላይ ፍጥረታት ሁሉ አንድ እግዚአብሔርን ያመሰግኑታል ፤ ተቀዳሚ ተከታይ የሌለው ልጁን አምላካችንንና መድኃኒታችንን ኢየሱስ ክርስቶስንም ያመሰግኑታል::

፳፩. የክርስቶስ ፈቃዱ ! የሚድኑት ይበዙ ዘንድ ከእነርሱም አንዱ ስንኳ እንዳይጠፋ ፤ ቤተ ክርስቲያንም እንዳትጐድል ነው፣ በአንድ ሐሳብ ሆነን እናመሰግነውና እንወድሰው ዘንድ በአንድ መንፈስም እንሰግድለት ዘንድ ፈቃዱ ነው::

፳፪. በንስሓ ፈጽማ የዳነችውን ነፍስ በቍጣና በብስጭት አትግደሉ::

፳፫. ወአንትሙሰ በሥነ ትዕግሥትክሙ ፈጽሙ ኵሎ ቃለ መጻሕፍት ወእመሰ ዘረውክሙ አባግዐ መርዔቱ ትከውኑ ጸላእያኒሁ ለእግዚአብሐር ወኢታኀጕሉ መሐስዐ ዘርእዮሙ ክርስቶስ ::

፳፬. ለቡ እንከ ኤጲስ ቆጶስ ከመ ኢይዘረዉ በምክንያተ ዚአከ አባግዐ መርዔቱ ለክርስቶስ እለ አስተጋባእናሆሙ በስብከተ ልሳናት እምኵለሄ በጻማ ወበድካም ፤ ወበኀዘን ወበትጋህ በረሀብ ወበጽምዕ ወበሥራኅ በሐዊረ ፍኖት ወበስደት ወምንዳቤ ወበተሞቅሖ::

፳፭. ወናሁ ገበርነ ሥምረቶ ለእግዚአብሐር ወመሳዕነ ውስተ ቤቱ አትክልተ እንተ ይእቲ ጉባኤ ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ዘእግዚአብሐር::

፳፮. ይትፌሥሑ ወይትኀሠዩ ውስቴታ እንዘ ይሴብሕዎ ለእግዚአብሐር ወይባርክዎ እለ ተጸውዑ ውስተ ሕይወት ዘለዓለም::

፳፫. እናንተ ግን በትዕግሥታችሁ ብዛት የመጻሕፍትን ሁሉ ቃል ፈጽሙ ፤ መንጋዎቹን ብትበትኑም የእግዚአብሔር ጠላቶች ትሆናላችሁ ፤ ክርስቶስ የጠበቃቸውን ግልገሎችንም አታስከፉብልሉ::

፳፬. ኤጲስ ቆጶስ ሆይ ! በቋንቋዎች በመስበክ ፤ በፍጹም ድካም ፤ በኀዘን ፤ በትጋት ፤ በረኃብና በጥም ፤ በችግር ፤ መንገድ በመሄድ ፤በስደትና በመከራ ፤ በእሥራት ከአራቱ ማእዘን የሰበሰብናቸው የክርስቶስ መንጋዎች በአንተ ምክንያት እንዳይበተኑ እንግዲህ አስተውል::

፳፭. እነሆ የእግዚአብሔርን ፈቃድ አደረግን በቤቱም ውስጥ ተክሎችን መሳን ፤ ይህችውም ቅድስት የእግዚአብሔር ቤተ ክርስቲያን የምዕመናን ጉባዔ ናት::

፳፮. ወደ ዘለዓለም ሕይወት የተጠሩም እግዚአብሔርን እያከበሩና እያመሰገኑ በውስጥዋ ደስ ይላቸዋል ፤ ኀሤትም ያደርጋሉ::



፳፯. ወአንትሙኒ አሕዛብ ግበሩ ማእከሌክሙ ፍቅረ ወሰላመ ከመ ትሑሩ ቤተ ክርስቲያኑ ለእግዚአብሐር በ፩ ልብ ወበእንተዝ ትረክቡ ዐስበ ሠናየ በኀበ እግዚአብሐር::

፳፰. ወአንተሰ ኤጲስ ቆጶስ ኩን ቅዱሰ ዘእንበለ ነውር ወኢትግበር ዘኢይደሉ ወኢትኩን መዓትመ ወኢጽልሕወ ወኢእኩየ ግዕዝ አላ ኩን ባሕቱ መገሥጸ ወረዳኤ ለእለ ይትኃጕሉ እምግብረ ሠናይ ወአጽንዖሙ ለሕዝብ ከመ ብእሴ እግዚአብሐር::

፳፱. ወሶበ ተጋባእክሙ ውስተ ቤተ ክርስቲያን አዝዞሙ ይሑሩ ፍኖተ ሠናየ ከመ ጠቢብ ሊቀ ሐመር ወለዲያቆናትኒ አዝዞሙ ይኩኑ ከመ ኖትያት ያንብርዎሙ ለአኀው ፩፩ ውስተ መካኖሙ በከመ ይደሉ በጽድቅ ወበንጽሕ ወእሙንቱ ኅቡረ ምስሌክሙ ውስተ ፩ ሐመር::

፴. ትኩን እንከ ከመዝ ቤተ ክርስቲያን ኑኃ መንገለ ምሥራቅ ወ፪ ሕዋራት ውስተ ገበዋቲሃ አምሳለ ሐመር ወይኩን መንበሩ ለኤጲስ ቆጶስ ርሡየ ማዕከለ ::

፳፯. እናንተም ሕዝቦች ወደ እግዚአብሐር ቤተ ክርስቲያን አንድ ልብ ሆናችሁ ትሄዱ ዘንድ በመካከላችሁ ፍቅርንና ሰላምን አድርጉ ፤ ስለዚህም በእግዚአብሐር ዘንድ በጎ ዋጋን ታገኛላችሁ::

፳፰. አንተም ኤጲስ ቆጶስ ሆይ ያለነውር ቅዱስ ሁን፤ የማይገባውንም አትሥራ ቁጡና ከዳተኛ ጠባየ ክፉም አትሁን፤ ነገር ግን ከበጎ ምግባር ወጥተው ለጠፉት የምትመክርና የምትረዳ ሁን ፤ የእግዚአብሐር ሰው እንደመሆንህም ሕዝቡን አጽናናቸው ::

፳፱. ወደ ቤተ ክርስቲያንም በተሰበሰባችሁ ጊዜ ብልህ የመርከብ ቀዛፊ እንደመሆንህ በጎ ጉዳናን ይሄዱ ዘንድ እዘዛቸው፤ ዲያቆናትም ወንድሞችን እያንዳንዳቸውን እንደሚገባ በእውነትና በንጽሕና በየቦታቸው ያስቀምጡአቸው ዘንድ እንደ ቀዛፊዎች እንዲሆኑ እዘዛቸው ፤ እነርሱም ከእናንተ ጋር በመርከብዋ ውስጥ በአንድነት ናቸው::

፴. እንግዲህ ቤተ ክርስቲያን እንዲህ ትሁን ርዝመቷ በምሥራቅ በኩል ይሁን ፤ በጎንና በጎንም በመርከብ አምሳል ሁለት ክፍሎች ይኑሩ፤የኤጲስ ቆጶሱ መንበርም በመካከል የተዘጋጀ ይሁን ::

፴፩. ወእምዝ ይንበሩ ቀሲሳን በየማኑ ወበፀጋሙ፡ኒ ዲያቆናት ይቁሙ ለተልእኮ እንዘ ቅኑታን አልባሲሆሙ ከመ ኖትያት።

፴፪. ወሕዝብሰ ይንበሩ ውስተ መካኖሙ በፍርሀት ወበረዓድ ወከማሁ አንስት ይንበራ እንተ ባሕቲቶን በአርምሞ።

፴፫. ወአናጉንስጢስ ይቁም ውስተ መካን ፣ ወያንብብ መጻ ሕፍተ ሙሴ ወኢያሱ ወልደ ነዌ ወመሳፍንት ወነገሥት ፣ ወሕፁፃን ወመጻሕፍተ፣እምድ ኅረ ፄዋዌ ግብአተ ባቢሎን ፣ ወኢዮብ ወሰሎሞን ፲ወ፰ተ ደቂቀ ነቢያት።

፴፬. ወእምዝ ያንብብ እም ውስተ መጻሕፍት በበ፪ ወይ ትነሣእ ፩ ወይስብክ በቃለ ዳዊት ወይትመጠዉ ሕዝብ ስብሐተ።

፴፭. ወእምዝ ያንብብ ግብረ ሐዋርያት ወመልእክተ እኁነ ጳውሎስ ፍቁርነ ፣ በግብር ዘጸ ሐፈ ወፈነወ ውስተ ኵሉ አብ ያተ ክርስቲያናት በረድኤተ መንፈስ ቅዱስ።

፴፩.ከዚህ በኋላ ቀሳውስት በቀኙ ይቀመጡ፣ በግራውም ዲያቆናቱ ልብሳቸውን ታጥቀው እንደ ቀዛ ፊዎች ይቁሙ።

፴፪. ሕዝቡ ግን በፍርሃትና በመንቀጥቀጥ በቦታቸው ይቀ መጡ ፤ እንዲሁም ሴቶች ብቻ ቸውን ዝም ብለው ይቀመጡ።

፴፫. አንባቢውም በቦታው ቁሞ አምስቱን የሙሴንና የነዌ ልጅ የኢያሱን ፣ የመሳፍንትንና የነ ገሥትን ፣ የዜና መዋዕልን መጻሕፍት ፣ ከባቢሎን ምርኮ መልስ በኋላ የተጻፉ መጻሕ ፍትን፣ የኢዮብንና የሰሎሞንን፣ የዐሥራ አምስቱን ደቂቀ ነቢ ያት መጻሕፍት ያንብብ ።

፴፬. ከዚህም በኋላ ከመጻሕፍት በየጥቂቱ ያንብብ ፣ አንዱም ተነ ሥቶ የዳዊትን መዝሙር ይስ በክ ፣ ሕዝቡም መዝሙሩን ይቀ በሉ ።

፴፭. ከዚህም በኋላ የእኛን የሐዋርያትን ሥራ ያንብብ ፣ በሥራ ወዳጃችን የሆነ ወንድ ማችን ጳውሎስ በመንፈስ ቅዱስ ረዳትነት ጽፎ ወደ አብያተ ክርስቲያናት የላከውንም መልእ ክት ያንብብ ።



፴፮. ወእምድኅረዝ ያንብቡ ቀሲሳን ወንጌለ አው ዲያቆናት ዘወሀብናክሙ አነ ማቴዎስ ወዮ ሐንስ ወዘሰበኩ ሉቃስ ወማርቆስ አዕርክቲሁ ለጳውሎስ ክቡር በግብር ወሠርዑ ለክሙ።

፴፯. ወሶበ ተነበ ወንጌል ይቁሙ ቀሳውስት ወዲያቆናት ወኵሉ ሕዝብ በዐቢይ ፍርሀት እስመ ጽሑፍ ዘይቤ አርምም እስራኤል ወአጽምዕ።

፴፰. ወእምዝ ቀሲሳን ይኩኑ ፩፩ ወያጽንዕዎሙ ለሕዝብ ወድኅረሰ ኤጲስ ቆጶስ ከመ ያድኅኖሙ በተግሣጽ።

፴፱. ወእምዝ ይቁሙ ዐጸውተ ኀዋኀው ኀበ ይበውኡ ዕደው ወያንብርዎሙ ውስተ መካ ኖሙ ከማሁ ዲያቆናዊትኒ ታቀ ውሞን ለአንስት ውስተ መካ ኖን።

፴፮. ከዚህም ቀጥሎ ቀሳውስት ወይም ዲያቆናት እኔ ማቴዎስና ዮሐንስ ጽፈን የሰጠናችሁን ፣ የከበረ የጳውሎስ የሥራ ወዳጆቹ ማርቆስና ሉቃስም የሰበኩትንና ለእናንተ የወሰኑትን ወንጌልን ያንብቡ።

፴፯. ወንጌልም በሚነበብበት ጊዜ ቀሳውስት ዲያቆናት ሕዝቡም ሁሉ በታላቅ ፍርሃት ይቁሙ ፣ እስራኤል ዝም ብለህ አድምጥ የሚል ጽሑፍ አለና።

፴፰. ከዚህም በኋላ ቀሳውስት አንድ አንድ እየሆኑ ሕዝቡን ያጽናኗቸው ፣ ከዚያም ቀጥሎ ኤጲስ ቆጶሱ ያድናቸው ዘንድ በምክር ያጽናናቸው።

፴፱. ከዚህም በኋላ በረኞች ወን ዶች በሚገቡበት ዘንድ ቁመው በቦታቸው ያስቀምጧቸው ፤ እን ደዚህም ዲያቆናዊት ሴት ሴቶ ቹን በቦታቸው ታቁማቸው።

፵. እመሰ ተረክበ እንዘ ይቀውም ውስተ ዘኢኮነ ሎቱ መካን ያስተ፡ነፍርዎ ዲያቆናት ወእ፡ምዝ ያግብዕዎ ውስተ መካኑ እስመ ዲያቆናትሰ ከመ ኖትያት፤ ወቤተ ክርስቲያን ከመ ሐመር፤ ወባሕቱ ኢኮነት ሐመረ አላ መርዔተ አባግዕ ፤ ወኖሎተ አባግዕሰ ይፈልጡ አባግዓ እምአጣሊ ወያነብር ዎሙ በበዘመዶሙ ወበበማ ኀበሮሙ ፤ ወከማሁ ይትረከቡ ሕዝብ በቤተ ክርስቲያን ኀቡረ በበነገዶሙ ወወራዙት ይቁሙ እንተ ባሕቲቶሙ::

፵፩. ወእመሰ አልቦ መካን ዘያገምሮሙ ይቁሙ ምስለ ሕዝብ ወአዕሩግኒ ይንበሩ እንተ ባሕቲቶሙ ወደቂቅኒ ይንበሩ ቅድመ አበዊሆሙ እንዘ ይጸንሕዎሙ::

፵፪. አዋልድኒ እንተ ባሕቲቶን ይንበራ፤ ወእመሰ አልቦ መካን ዘያገምር ይቁማ ድኅረ ውሉ ባት ፤ ወደናግል ወመበለታት ወመላሕቅታት ይቁማ ቅድመ ኵሎን አንስት ፤ ወእለሰ ቦቶን ምት ወደቂቅ እንተ ባሕቲቶን ይንበራ ::

፵. ለእርሱ ባልሆነ ቦታ ቁሞ ቢገኝ ግን ዲያቆናት ያሳፍ ሩት ፤ ከዚህም በኋላ ወደቦ ታው ይመልሱት ፤ ዲያቆናት እንደ ቀዛፊዎች ናቸውና፤ ቤተ ክርስቲያንም እንደ መርከብ ናትና ፤ ነገር ግን ቤተ ክርስቲ ያን መርከብ አይደለችም የበ ጎች መንጋ ናት ፤ እረኞች በጎ ችን ከፍየሎች ለይተው በየወ ገናቸውና በየመንጋቸው ያስማ ሯቸዋል ፤ እንደዚሁም ሕዝቡ በቤተክርስቲያን በየወገናቸው ይገኙ ፤ ጐልማሶችም ብቻቸ ውን ይቁሙ::

፵፩. የሚበቃቸው ቦታ ባይኖር ግን ከሕዝቡ ጋራ ይቁሙ ፤ ሽማግሌዎችም ብቻቸውን ይቀ መጡ፤ ወንዶች ልጆችም እየተ ጠባበቋቸው በአባቶቻቸው ፊት ይቀመጡ ::

፵፪. ሴቶች ልጆችም ብቻቸ ውን ይቀመጡ ፤ ቦታ ባይኖር ግን ባገቡት ሴቶች ኋላ ይቁሙ፤ ደናግልና መበለቶች ባልቴቶችም በሴቶች ፊት ይቁሙ ፤ ባልና ልጅ ያላቸው ሴቶች ግን ብቻቸውን ይቀ መጡ::



፵፫. መፍትው ለዲያቆናት ይሥርዕዎሙ ለለ፩፩ ወኢይት ዐደዉ ውስተ መንበረ ካልኡ ወይጠይቁ ንብረቶሙ ወሕይወ ቶሙ ለሕዝብ ውስተ ቤተ ክር ስቲያን ከመ ኢይኑሙ ወኢይ ትሐከዩ ጸልዮ አላ ያስተ ሐይጹ::

፵፬. ወእመቦ ዘይትረከቡ በሰ ሐቅ ወበዛውዕ ይገሥጾሙ ወይ ረስዮሙ ያርምሙ::

፵፭. መፍትውኬ ለነ ንቁም ውስተ ቤተ ክርስቲያን በፍ ርሀት ወበረዓድ ወንረሲ ሕሊናነ ለአጽምዖ ቃለ መጻ ሕፍት ::

፵፮. ወሶበ ይጸርሕ እንዘ ይብል ይፃኡ ንኡሰ ክርስቲያን መምህራን ወእለ ውስተ ንስሓ ወኵሉ ሕዝብ ይትነሥኡ ወይ ነጽሩ መንገለ ምሥራቅ ወይ ሰአልዎ ለእግዚአብሔር ዘሀ ልው ውስተ ኵሉ መካን ያግ ብኦሙ ውስተ ዘቀዳሚ መካን ኀበ ገነተ ትፍሥሕት ዘወጽአ እምኔሃ ቀዳሚ ብእሲ አዳም ኀበ ሠምረ ምክረ አርዌ ምድር ወዐለወ ትእዛዘ እግዚአብሔር::

፵፫. ለዲያቆናት እያንዳንዱ ወደ ሌላው የሁለት መቀመጫ እንዳ ይተላለፉ ያስተናብሩአቸው ሕዝ ቡም እንዳይተኙ ለጸሎትም ቸል እንዳይሉ በቤተ ክርስቲያን አነ ዋወራቸውንና ሕይወታቸውን ይረዱ ዘንድ አገባብ ነው::

፵፬. ነገር ግን በሳቅና በዋዛ የሚገኙ ሰዎች ቢኖሩ ዲያቆኑ ይምክራቸው ፤ ዝም እንዲሉም ያድርጋቸው::

፵፭. ለእኛም በመፍራትና በመ ንቀጥቀጥ በቤተ ክርስቲያን እንድንቆም አሳባችንንም የመጻሕ ፍትን ቃል ወደ መስማት እንድ ናደርግ ይገባል::

፵፮. ንዑሰ ክርስቲያን ይውጡ ብሎ ዲያቆኑ አሰምቶ በሚናገ ርበት ጊዜ መምህራንና በንስሐ ያሉ ሰዎች ሕዝቡም ሁሉ ቆመው ወደ ምሥራቅ ይመልከቱ ፤ የእ ባብ ምክርን ሰምቶ የእግዚአብ ሔርን ትእዛዝ ያፈረሰ የቀደመ ሰው አዳም ከእርሷ ወደ ወጣ ባት ወደ ደስታ ገነት ወደ ቀደ መው ቦታ ይመልሳቸው ዘንድ በቦታው ሁሉ የሚኖር እግዚአብ ሔርን ይለምኑት::

፵፯. ወእምዝ ይትነሥኡ ቀሳውስት ወያዕርጉ መሥዋዕተ ለእግዚአብሔር በፍርሀት ወበረዓድ፡፡

፵፰. ወእምዝ ይትነሥኡ ላዕካን ወየአዝዝዎሙ ለሕዝብ ከመ ያርምሙ፡፡

፵፱. ወዲያቆን ዘይቀውም በየማኑ ለኤጲስ ቆጶስ ከመዝ ይበል ለሕዝብ ኢያንብር ወኢመኑሂ ቂመ ወጽልአ ወቅንአተ ላዕለ ቢጹ፡፡

፶. ወእምድኅረዝ ይትአምኑ ሕዝብ በበይናቲሆሙ በአምኃ ቅድሳት ፤ ወከማሁ አንስትኒ ይትአምኃ በበይናቲሆን ፤ ወባሕቱ ኢይትአምኑ በጕኅሉት ከመ ይሁዳ አስቆሮታዊ ዘሰአሞ ለእግዚእነ ወአግብኦ በዓመፃ፡፡

፶፩. ወእምድኅረዝ ይጸሊ ዲያቆን ወይስአል በእንተ ኵላ ዓለም ወኵሉ ዘውስቴታ በእንተ ፍሬ ምድር በእንተ ንጉሥ በእንተ ካህናት በእንተ ሰላማ ለቅድስት ቤተ ክርስቲያን እንተ ሐዋርያት፡፡

፵፯. ከዚህም በኋላ ቀሳውስት ተነሥተው በመፍራትና በመንቀጥቀጥ መሥዋዕትን ለእግዚአብሔር ያቅርቡ፡፡

፵፰. ከዚህም በኋላ ዲያቆናት ተነሥተው ሕዝቡን ዝም ይሉ ዘንድ ይዘዟቸው፡፡

፵፱. በኤጲስ ቆጶሱ ቀኝ የሚቆመው ዲያቆንም እንደዚህ ይበል ፤ ማንም ቂምንና ጥልን ቅንአትንም በወንድሙ ላይ አያኑር፡፡

፶. ከዚህም በኋላ ሕዝቡ እርስ በርሳቸው በተቀደሰ ሰላምታ እጅ ይነሣሡ ፤ ሴቶችም እንዲሁ እርስ በርሳቸው በተቀደሰ ሰላምታ እጅ ይነሣሱ፣ ነገር ግን ጌታችንን እንደሳመውና በዐመፅ እንዳስያዘው የአስቆሮቱ ይሁዳ በተንኮል እጅ አይነሣሡ ፡፡

፶፩. ከዚህም በኋላ ዲያቆኑ ስለ ዓለም ሁሉ በውስጧም ስለ አሉ ስለ ምድር ፍሬ ስለንጉሥ ፤ ስለ ካህናት ፤ ስለ ሰላም ፤ ስለ ሐዋርያዊት ቅድስት ቤተ ክርስቲያንም ሰላም ይጸልይ፡፡



፶፪. ወእምድኅረዝ ይስአል ወያስተብቍዕ ሊቀ ካህናት ከመ ይኩን ሰላም ላዕለ ሕዝብ፡፡

፶፫. ወእምዝ ይባርኮሙ በከመ አዘዞሙ ሙሴ ይባርኩ ካህናት ላዕለ ሕዝብ እንዘ ይብሉ ከመዝ ለይባርክ እግዚአብሔር ወይዕቀብከ ወያርኢ ገጾ ላዕሌከ ወይምሐርከ ወየሀብከ ሰላመ[፳] ፡፡

፶፬. ወእምድኅረዝ ይስአል ኤጲስ ቆጶስ ወይበል አድኅን ሕዝበከ ወባርክ ርስተከ ሪዐዮሙ ወአልዕሎሙ እስከ ለዓለም ወእቀባ ለቤተ ክርስቲያንከ ቅድስት እንተ አጥረይካ ወቤዘውካ በደሙ ክቡር ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወጸዋዕካ ትኩን ማኅደረ ለነገሥት ወለካህናት ወለዘመድ ንጹሕ ወለሕዝብ ቅዱስ፡፡

፶፭. ወእምድኅረ ተመጠዉ ካህናት ምሥጢራተ ይዕቀቡ ከመ ኢይባኡ እለ ኢኮኑ ምእመናን፡፡

፳ ዘኍል ፮:፳፫-፳፮

፶፪. ከዚህም በኋላ የካህናቱ አለቃ በሕዝቡ ላይ ሰላም ይሆን ዘንድ ይማልድ ፡፡

፶፫. ከዚህም ቀጥሎ ሙሴ ካህናቱ ሕዝቡን ይባርኩ ዘንድ እንዳዘዛቸው እንዲህ እያለ ይባርካቸው ፤ እግዚአብሔር ይባርክህ ፤ ይጠብቅህም ፊቱንም ያብራልህ ፤ ይራራልህም ሰላምንም ይስጥህ ፡፡

፶፬. ከዚህም በኋላ ኤጲስ ቆጶሱ ሕዝብህን አድን ፤ ርስትህንም ባርክ እስከ ዘለዓለምም ጠብቃቸው ፤ ከፍ ከፍም አድርጋቸው ፤ በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ደም ገንዘብ ያደረግሃትና የዋጀሀት ፤ ለነገሥትና ለካህናት ለንጹሕ ወገንና ለቅዱስ ሕዝብም ማደርያ ትሆን ዘንደ የጠራሃት ቤተ ክርስቲያንህንም ጠብቃት እያለ ይጸልይ ፡፡

፶፭. ካህናት ሥጋውንና ደሙን ከተቀበሉ በኋላ ያላመኑ ሰዎች ወደ ቤተ ክርስቲያን እንዳይገቡ ይጠብቁ፡፡

፶፮. ወእምዝ ይቁሙ ሕዝብ
ወአንስትኒ እንዘ ይትገለበባ
ርእሶን ይስፍሑ እደዊሆሙ
ወይስአሉ ስርየተ ወይትመ
ጠዉ ሥጋሁ ቅዱሰ ወደሞ
ክቡረ ።

፶፯. ወእመቦ ዘመጽኡ አኀው
አው አኃት እምርኁቅ ብሔር
ይጠይቅ ሕይወቶሙ ዲያቆን
ወይለቡ ሃይማኖቶሙ።

፶፰. ወእመሰ ቦሙ ትምህርተ
ርትዕት ሃይማኖት ይትወከ
ፎሙ ወይባኡ ቤተ ክርስቲያን
ወእመሰ ዕልዋን እሙንቱ
ኢይትወከፎሙ ይባኡ።

፶፱. ወእመሰ መጽአ ቀሲስ
እምርኁቅ ብሔር ይትወከ
ፍዎ ቀሳውስት ወናሁ እመ
ውእቱ ዲያቆን ይትወከፍዎ
ዲያቆናት።

፷. ወእመሂ መጽአ ኤጲስ
ቆጶስ እንግዳ ይትወከፎ ኤጲስ
ቆጶስ ዘከማሁ ወይንበር ምስ
ሌሁ ወያክብሮ ወእምዝ ይስ
አሎ ከመ ይምሀሮሙ ወይገሥ
ጾሙ ለሕዝብ እስመ ይቤ
መጽሐፍ ኢይከብር ነቢይ በሀ
ገሩ[፱]፣ ወያስተብቍዕዎ ከመ
ያዕርግ መሥዋዕተ ወእመሰ
በምክንያተ ፍርሀት አበየ ፈድ
ፋደ ያስተብቍዕዎ ከመ ይጸጉ
በረከተ ለሕዝብ።

፶፮. ከዚህም በኋላ ሕዝቡ
ይቁሙ ፣ ሴቶችም ራሳቸውን
ተሸፍነው ይቁሙ ፣ እጆቻቸ
ውንም ዘርግተው ይቅርታን
ይለምኑ ፣ ቅዱስ ሥጋውንና
ክቡር ደሙንም ይቀበሉ ።

፶፯. ከሩቅ ሀገር የመጡ ወንድ
ሞች ወይም እኅቶች ቢኖሩ
ዲያቆኑ አኗኗራቸውን ይጠይቅ፣
ሃይማኖታቸውንም ይረዳ።
፶፰. የቀናች ሃይማኖት ትም
ህርት ቢኖራቸው ግን ይቀበላ
ቸው ፣ ወደ ቤተ ክርስቲያንም
ይግቡ ፣ ከሐዲዎች ቢሆኑ ግን
ይገቡ ዘንድ አይቀበላቸው።
፶፱. ቄስ ከሩቅ ሀገር ቢመጣ ግን
ቀሳውስት ይቀበሉት ፣ ዲያቆ
ንም ቢሆን ዲያቆናቱ ይቀ
በሉት።

፷. እንግዳ ኤጲስ ቆጶስም
ቢመጣ እንደ እርሱ ያለው
ኤጲስ ቆጶስ ይቀበለው፣ ከእርሱ
ጋራም ይቀመጥ ያክብረውም፣
ከዚህም በኋላ ሕዝቡን ያስተም
ራቸውና ይመክራቸው ዘንድ
ይጋብዘው መጽሐፍ ነቢይ
በሀገሩ አይከብርም ብሏልና፣
መሥዋዕትንም ያሳርግ ዘንድ
ይለምኑት ፣ በፍርሃት ምክንያት
አይሆንም ቢል ግን ለሕዝቡ
በረከትን ይሰጥና ያሳድር ዘንድ
አብዝተው ይማልዱት።

፱ ሉቃ ፬:፳፬-፳፯ ፣ ዮሐ. ፬ - ፵፬



፷፩. ወእመሰ ቦ ዘመጽአ
እንከ ኀቤከ እንግዳ አው
እምሰብእ ብሔር እንዘ ይለብስ
አስኬማ ሠናየ ዘምሉእ ሞገሰ
አንተ ኤጲስ ቆጶስ ንግሮ ቃለ
እግዚአብሔር ፣ ወሶበ ሰማዕከ
እንዘ ይሜህሩ ወያነብቡ መጽ
ሐፈ ኢታጽርዕ ተቀንዮ ግብ
ርከ ።

፷፪. መፍትው ይትወከፍዎሙ
ለአናግድ አኀው ወያብእዎሙ
ወያክብርዎሙ።

፷፫. ወእመሰ ቦ ዝንቱ ወኢያከ
ብር ነግደ መጺአ ዲያቆን ይገ
ሥጾ ወያቅሞ ድኅረ ሕዝብ ከመ
ርእዮሙ ካልኣን ይፍርሁ ።

፷፬. ወእመሰ መጽአ ኀቤክሙ
ነዳይ ወሬዛ አው አረጋዊ ይት
ወከፎሙ ዲያቆን በፍሡሕ
ልብ ወያንብሮሙ ለለ፩፩
ውስተ መካኑ በከመ ይደሉ
ዘእንበለ ነሢአ ገጽ አላ ትኩን
መልእክትክሙ እንተ ታሠምሮ
ለእግዚአብሔር ።
፷፭. ወዲያቆናዊትኒ ከማሁ
ትግበር ለአንስት ምስለ አብዕ
ልት ወነዳያን።

፷፩. አንተ ኤጲስ ቆጶስ ሆይ!
እንግዲህ እንግዳ ሰው ወይም
ከሀገር ሰው ባለሚልነትን
የተሞላ መልካም የምንኩስና
ልብስን ለብሶ ወደ አንተ ቢመጣ
የእግዚአብሔርን ቃል ንገረው ፤
መጻሕፍትን ሲያነቡና ሲያስ
ተምሩ በምትሰማበት ጊዜ ፣
የተግባርህን አገለግሎት አታ
ቋርጥ ።

፷፪. እንግዶች ወንድሞችን
ተቀብለው ያስገቧቸውና ያከብ
ሯቸው ዘንድ አገባብ ነው።

፷፫. ትዕቢተኛ ቢኖር ፣ እንግ
ዳንም ባያከብር ዲያቆኑ መጥቶ
ይምከረው ፣ ሌሎቹ አይተው
እንዲፈሩም ከሕዝቡ በስተኋላ
ያቁመው፤

፷፬. ወደ እናንተ ድኃ ፣ ጐል
ማሳ ፣ ወይም ሽማግሌ ቢመጣ
ግን ዲያቆኑ በደስተኛ ልብ
ይቀበላቸው ፣ እያንዳንዱንም
እንደሚገባ ፊት አይቶ ሳያዳላ
በየቦታው ያስቀምጣቸው ፣ ነገር
ግን አገልግሎታችሁ እግ
ዚአብሔርን ደስ የምታሰኘው
ትሁን።
፷፭. እንደዚሁም ዲያቆናዊቲቱ
ከባለጸጎችና ድሆች ጋራ ለሴ
ቶች ታድርግ ።

፷፮. ገሥጾሙኬ ኤጲስ ቆጶስ ለሕዝብ ወአዝዞሙ ይምጽኡ ኀበ ቤተ ክርስቲያን መዓልተ ወሌሊተ ወግሙራ ኢይርኀቁ እምኔሃ ወኢይኩኑ ሕዝብ ሕፁፃነ እምኔሃ እስመ አባሉ ለክርስቶስ እሙንቱ።

፷፯. ወአኮ በእንተ ካህናት ባሕቲቶሙ ዘንቤ ዘንተ አላ በእንተ ኵሉ ሕዝብ ከመ ይለብዉ ለለ፩፩ ቃለ እግዚአብሔር እስመ ይቤ እግዚእነ ፤ ወዘሰ ኢሀሎ ምስሌየ ዕድውየ ውእቱ ወዘኢይትጋባእ ምስሌየ ይዘርወኒ[፲] ።

፷፰. ኢትትሐከዩ እንከ እስመ አካሉ ለክርስቶስ አንትሙ ወኢትትፈለጡ እምሥጋሁ ወኢታብድሩ ትካዘ ዝ ዓለም እምትእዛዛቲሁ ለእግዚአብሔር ተጋብኡ ውስተ ቤተክርስቲያን ነግሀ ወሠርከ ሰብሑ ወዘምሩ ወአንብቡ መዝሙረ ዳዊት ዘ፷ወ፪ ፤ ወዓዲ ዘ፻ ወ፵ ።

፷፱. ወፈድፋደሰ በሰንበተ ክርስቲያን እንተ ይእቲ ትንሣኤሁ ቅድስት አዕርጉ ስብሐተ ወአኰቴተ ወክብረ ለእግዚአብሔር ዘፈጠረ ኵሎ በወልዱ ኢየሱስ ክርስቶስ ዘፈነወ ኀቤነ ወሠምረ ይሕምም በፈቃዱ ወተቀብረ በሥምረቱ ውስተ ምድር ወተንሥአ እሙታን።

[፲] ማቴ፡ ፲፪ - ፴

፷፮. ኤጲስ ቆጶስ ሆይ ! ሕዝቡን ምከራቸው ፤ በሌሊትና በቀንም ወደ ቤተ ክርስቲያን እንዲመጡ፤ፈጽመውም ከእርሷ እንዳይርቁ ፤ ሕዝቡም ከእርሷ ያነሱ እንዳይሆኑ እዘዛቸው ፤ እነርሱ የክርስቶስ አካላት ናቸውና።

፷፯. ይህንም የምንለው ስለ ካህናት ብቻ አይደለም ፤ እያንዳንዱ የእግዚአብሔርን ቃል ያስተውሉ ዘንድ ፤ ስለ ሕዝቡም ሁሉ ነው እንጂ፤ ጌታችን ከእኔ ጋራ ያልሆነ ባላጋራዬ ነው፤ከእኔም ጋር የማይሰበስብ ይበትናል ፤ ይቃወመኛል።

፷፰. እንግዲህ ቸል አትበሉ ፤ የክርስቶስ አካል ናችሁና ፤ ከእርሱም አካል አትለዩ ፤ ከእግዚአብሔርም ትእዛዝ የዚህን ዓለም ግዳጅ አትምረጡ፤ በነግህና በሠርክም በቤተ ክርስቲያን ተሰብስባችሁ ስልሳ ሁለተኛውንና ዳግመኛም መቶ አርባኛውን የዳዊትን መዝሙር አንብቡ ዘምሩ አመስግኑም።

፷፱. ይልቁንም ቅድስት ትንሣኤው በተደረገባት በክርስቲያን ሰንበት ወደኛ በላከው በፈቃዱም መከራን ይቀበል ዘንድ በወደደ ፣ በፈቃዱም በምድር በተቀበረ ከሙታንም ተለይቶ በተነሣው በልጁ በኢየሱስ ክርስቶስ ሁሉን ለፈጠረ ለእግዚአብሔር ምስጋናንና ፍጹም ክብርን አቅርቡ።



፸. ወእመሰ ኢመጻእክሙ ውስተ ቤተ ክርስቲያን ምንተ ታመክንዩ ወታወሥእዎ ለእግዚአብሔር ፤ እስመ በዛቲ ዕለት ሰንበተ ክርስቲያን መፍትው ንስማዕ ስብከተ ትንሣኤሁ ቅድስት ፤ ወንዘክር ሕማማቲሁ፤ ወንግበር ተዝካሮ ፤ ወናንብብ መጻሕፍተ ነቢያት፤ ወወንጌለ ቅዱሰ ወንግበር መሥዋዕተ ወቍርባነ መብልዐ መንፈሳዌ።

፸፩. ወእመሰ ኢተጋሀክሙ መዓልተ ወሌሊተ ወኢገበርክሙ በከመ ዘንቤ ትከውኑ አባስያኒሁ ለእግዚአብሔር ፤ ወጸላእያኒሁ ፤ እስመ አብደርክሙ ተድላ መብልዐ ፤ ወስታየ ወፍግዓ ዘይበሊ ወይማስን ፤ ወኀደግሙ ዘኢይበሊ ወኢይማስን።

፸፪. ወለእለ ገብሩ ከመዝ ይቤሎሙ እግዚአብሔር ይኄይሱ እምኔክሙ አብዳን ሕዝብ በከመ ጸዐላ ለኢየሩሳሌም፤ ወይቤላ ሰዶም ትኄይስ እምኔኪ ።

፸. ወደ ቤተ ክርስቲያን ባትመጡ ግን ምን ታመካኛላችሁ? ለእግዚአብሔርስ ምን ትመልሱለታላችሁ ? በዚህች በክርስቲያን ሰንበት ዕለት የቅድስት ትንሣኤውን ስብከት እንሰማ ዘንድ ፤ መከራዎቹንም እናስብ ዘንድ ፤ መታሰቢያውንም እናደርግ ዘንድ ፤ የነቢያትን መጻሕፍትና ቅዱስ ወንጌልንም እናነብ ዘንድ ፤ መንፈሳዊ ምግብ የሚሆን መሥዋዕትንና ቍርባንንም እናቀርብ ዘንድ ይገባልና።

፸፩. በሌሊትና በቀን ባትተጉ ፤ እንዳልናችሁም ባታደርጉ ግን ፤ እግዚአብሔርን የምትበድሉትና የምትጠሉት ትሆናላችሁ ፤ የሚያልፍና የሚጠፋ ተድላን መብልንና መጠጥን ፤ የሚያልፍ የሚጠፋ ደስታንም መርጣችሁ፤ የማያልፈውንና የማይጠፋውን ትታችኋልና ።

፸፪. እንደዚህም የሚያደርጉትን እግዚአብሔር ከናንተ ይልቅ አላዋቆች የሆኑት ሕዝብ ይሻላሉ አላቸው ፤ ይህም ኢየሩሳሌምን ከአንቺ ይልቅ ሰዶም ትሻላለች ብሎ እንደ ነቀፋት ።

፸፫. ናሁኬ ርእይዎሙ ለአብዳን ኵሎ አሚረ እንዘ ይነቅሐ ወይተግሁ ወየሐውሩ ፍጡነ ኀበ እለ ኢይበቍዑ አማልክት፤ ወይሰግዱ ሎሙ ፤ ወይ ስእሉ ኵሎ ትካዞሙ ፤ ወይት ጋብኡ በዕለተ በዓሎሙ ኀቡረ ንዑሶሙ ወዐቢዮሙ ፤ ወአኮስ እሉ ባሕቲቶሙ አላ ካልኣንሂ ይመጽኡ እምርኁቅ ብሔር ፣ ወያመልክዎሙ ፤ ወይትቀነዩ ሎሙ፡፡

፸፬. ወእመሰ አብዳን አይሁድ ዕልዋን ወመናፍቃን ይትቀነዩ ሰዱሰ ዕለተ ፤ ወየዐርፉ በሳብዕት ዕለት ፤ ወእምዝ ይትጋብኡ ውስተ ምኵራባቲሆሙ ፤ ወይገብሩ በዓለ ለጣዖታት ወያዐብይዎሙ ወያከብርዎሙ ለእለ አልቦሙ ነፍስ፤ ወመንፈስ ፤ ወኢይበቍዑ ወኢምንተኒ ፤ ወይትሜክሑ ፤ ወይብሉ ፤ ንሕነ እሙንቱ አይሁድ፤ ወእለሰ ይገብሩ ከመዝ፤ ወይትጋብኡ ኵሎ ጊዜ ፤ ወይትቀነዩ ለባዕዳን እለ አልቦሙ ባቍዕ ፤ እፎኬ አንትሙ እለ ነሣእክሙ ጸጋ በኀበ እግዚአብሔር አምላክ ትትሐከዩ ፤ ወታጸርኡ ቅኔ ቤተ ክርስቲያን ፡፡

፸፫. እነሆ ሁልጊዜ ነቅተውና ተግተው ወደማይጠቅሙ ጣዖታት ፈጥነው ሲኼዱና ሲሰግዱላቸው አላዋቆችን ተመልከቷቸው፤ ትንሾቹም ትልቆቹም በበዓላቸው ቀን በአንድነት ተሰብስበው ግዳጃቸውን ሁሉ ይለምናሉ ፤ እኒህ ብቻ አይደሉም፤ ነገር ግን ሌሎችም ከሩቅ ሀገር መጥተው ያመልኳቸዋል ፤ ይገዙላቸዋልም፡፡

፸፬. አላዋቆች ፤ ወንጀለኞችና ተጠራጣሪዎች አይሁድ ስድስቱን ቀን ሠርተው በሰባተኛይቱ ቀን የሚአርፉ ከሆነ ፤ ከዚህም በኋላ በምኵራቦቻቸው ተሰብስበው ለጣዖታት በዓልን የሚያደርጉ ነፍስና እስትንፋስ የሌላቸውን ምንም ምን የማይጠቅሙ ጣዖታትን የሚያከብሯቸው ከሆነ ፤ ታማኞች አይሁድ እኛ ነን እያሉ የሚመኩ ከሆነ ፤ እንደዚህ የሚያደርጉም ሁልጊዜ የሚሰበሰቡ ጥቅም ለሌላቸው ጣዖታትም የሚያገለግሉ ከሆነ ፤ በፈጣሪ እግዚአብሔር ዘንድ ጸጋን የተቀበላችሁ እናንተማ እንዴት ትሰንፋላችሁ? ቤተ ክርስቲያን ማገልገልንስ እንዴት ታስታጉላላችሁ?



፸፭. ወእመሰ ርኁቅሙ እምቤተ ክርስቲያን ተኀጕሉ ተስፋክሙ ፤ ወትቀብፁ ተስፋ መድኃኒትክሙ ፤ ወትከውኑ ዕልዋነ ፤ ወትትገሀሡ እምሥናያት ወትከውኑ እኩያነ፡፡

፸፮. ናሁ ይቤ እግዚአብሔር በኤርምያስ ነቢይ ኀደጉ ሕዝብየ ሕግየ ዘወሀብክዎሙ ቅድመ ገጾሙ ፤ ወኢሰምዑ ቃልየ ፤ ወሖሩ ወተለዉ ፍትወተ ልቦሙ ወተለዉ ጣዖተ ዘመሀርዎሙ አበዊሆሙ፡፡[፲፩]

፸፯. ወዓዲ ይቤ አጽደቀት ነፍሰ ዕልውት እስራኤል እምነ ኀሥርት ይሁዳ ፤ ወለኖሎቶሙ ሰደድዎሙ ውስተ አድባር ፤ ወገደፍዎሙ ፤ ወአንጌገዩ ውስተ አውግር[፲፪]፡፡

፸፰. ምንተ ያመክንዩ እለ ይትሀከዩ ሐዊረ ቤተ ክርስቲያን ወይወፅኡ እምኔሃ በጊዜ ጸሎት አየ ጊዜ ይሰምዑ መድኃኒተ ነፍሶሙ ፤ ወምንተ ያወሥእዎ ለእግዚአብሔር፡፡

፲፩ ኤርም. ፱፡ - ፲፬
፲፪ ሕዝ. ፰ - ፲፮

፸፭. ከቤተ ክርስቲያንም ብትርቁ ግን ተስፋችሁን ታጣላችሁ፤ የመዳናችሁንም ተስፋ ትቆርጣላችሁ ፤ ወንጀለኞችም ትሆናላችሁ ፤ ከበጎ ነገርም ትርቃላችሁ ፤ ክፉዎችንም ትሆናላችሁ፡፡

፸፮. እነሆ እግዚአብሔር በነቢዩ በኤርምያስ እንዲህ አለ ፤ ወገኖቼ በፊታቸው የሰጧቸውን ሕጌን ትተዋል ፤ ቃሌንም አልሰሙም፤ የልቡናቸውንም ፈቃድ ተከትለው ኖሩ፤አባቶቻቸው ያስተማሯቸው ጣዖትንም ተከተሉ ፡፡

፸፯. ዳግመኛም ከወራዳዪቱ ይሁዳ ይልቅ ከዳተኛዋ እስራኤል ራስዋን አጸደቀች ፤ እረኞቻቸውንም ወደ ተራራዎች አባርረው ጣሏቸው ፤ እነርሱም በየኮረብታው ተቅበዘበዙ፡፡

፸፰. ወደ ቤተ ክርስቲያን መሄድን ቸል የሚሉ ሰዎች ፤ በጸሎት ጊዜም ከእርሷ የሚወጡ ሰዎች ምን ያመካኛሉ? የነፍሳቸውንስ ድኅነት ምን ጊዜ ይሰማሉ ? ለእግዚአብሔርስ ምን ይመልሱለታል?

፸፱. ለብዉ እንከ ከመ ቅኔ ሆሙ ለመሃይምናን ህልው ምስሌሆሙ ወበጽድቅ ዘውእቱ አምልኮ እግዚአብሔር::

፹. ኢይኩን ግብርክሙ ወፃማ ክሙ እምትካዘ ዝንቱ ዓለም ኃላፊ ዘይበሊ ወይማስን ፤ አላ ይኩን ሕሊናክሙ ኀበ እግ ዚአብሔር በከመ ይቤ እግዚእነ ኢተሐልዩ ለመብልዕ ኀላፊ ዘይበሊ ወይማስን አላ ፤ ለመ ብልዕ ዘይነብር ለሕይወት ዘለ ዓለም::[፲፫]

፹፩. ወዓዲ ይቤ እስመ ግብር ዘያሠምሮ ለእግዚአብሔር ዝ ውእቱ ከመ ትእመኑ በዘፈነዎ ኀቤክሙ ::

፹፪. ዑቁኬ እንከ ኢትርኀቁ እምቤተ ክርስቲያኑ ለእግዚአ ብሔር ፤ ወኢትትልዉ ዐሠ ሮሙ ለዕልዋን ፤ ወመናፍቃን ወመምልክያነ ጣዖት ማኅበረ አይሁድ::

[፲፫] ዮሐ. ፮ - ፳፯ - ፳፱

፸፱. የምእመናን አገልግሎታ ቸው ከእነርሱ ጋራ እንደሆነ አስተውሉ ፤ በእውነትም እግ ዚአብሔርን ማምለክ ይህ ነው::

፹. ሥራችሁና ድካማችሁም ከሚጠፋና ከሚበላሽ ከኀላ ፊው ከዚህ ዓለም ግዳጅ አይ ሁን ፤ ነገር ግን ጌታችን ለዘለ ዓለም ሕይወት ለሚኖር መብል እንጂ ፤ ለሚያልፍ ለሚጠፋና ለሚበላሽ መብል አትጨነቁ እንዳለ ፤ ሐሳባችሁ ወደ እግዚአ ብሔር ይሁን::

፹፩. ዳግመኛም እንዲህ አለ ፤ እግዚአብሔርን ደስ የሚአሰኘው ሥራ ይህ ነው፤ ይኸውም ወደ እናንተ በላከው በልጁ ታምኑ ዘንድ ነው::

፹፪. እንኪያስ ከእግዚአብሔር ቤተ ክርስቲያን እንዳትርቁ እወቁ፣ የወንጀለኞችን ፣ የመ ናፍቃንን፣የተጠራጣሪዎችን፣ጣዖ ትንም የሚአመልኩትን የአይሁ ድንም ፍለጋ አትከተሉ::



፹፫. ኢትሑሩ ቤተ አማልክተ አጋንንት ፤ ወኢትኅበሩ ምስለ ቀታልያነ ክርስቶስ ፤ ወኢት ባኡ ውስተ ምኵራብ ዕልዋን::

፹፬. ኢሰማዕክሙኑ ዘይቤ ፤ ኢነበርኩ ውስተ ዐውደ ከንቱ፤ ወኢቦእኩ ምስለ ዐማጽያን ፤ ጸላእኩ ማኅበረ እኩያን ፤ ወኢይነብር ምስለ ዐማጽያን ወጽልሕዋን[፲፬]::

፹፭. ወካዕበ ይቤ ፤ ብፁዕ ብእሲ ዘኢሖረ በምክረ ረሲዓን ፤ ወዘኢቆመ ውስተ ፍኖተ ኃጥ አን ፤ ወዘኢነበረ ውስተ መን በረ መስተሣልቃን ዘዳዕሙ ሕገ እግዚአብሔር ሥምረቱ፤ ወዘሕጎ ያነብብ መዓልተ ወሌ ሊተ[፲፭]::

፹፮. ወአንተሰ ኅደገ ማኅበረ ክርስቲያን ፤ ወመነንከ ቤተ ክርስቲያኑ ለእግዚአብሔር ፤ ወኢዐቀብከ ሕጎ ወሥርዓቶ ፤ ወተለውከ ፍኖተ ፈያት፤ ወረ ሰይከ ርኩሰ ከመ ዘንጹሕ::

፹፯. ወተዐረከ ምስለ እለ ተፈ ልጡ እምኔከ ፤ ወረሰይከ ንብረተከ ምስለ አረማውያን ፤ ወአጽማዕከ በእዝንከ ቃለ ተው ኔት ዘምሉእ ኵሎ ርኵሰ ወነገረ ከንቱ ዘአልቦ ባቍዕ::

[፲፬] መዝ. ፳፭ : ፬ - ፭

[፲፭] መዝ. ፩ - ፪

፹፫. የአጋንንት ማደሪያ ወደሚ ሆኑ ጣዖታት ቤት አትሒዱ፣ ክርስቶስን ከገደሉ ሰዎች ጋራም አትተባበሩ፤ ወደ ወንጀለኞች ምኵራብም አትግቡ::

፹፬. በከንቱ አደባባይ አልተቀ መጥኩም ከበደለኞችም ጋራ አልገባሁም፤ የክፉዎችንም ማኅ በር ጠላሁ፤ ከዐመፀኞችና ከሽ ንጋዮች ጋራም አልቀመጥም ያለውን አልሰማችሁም?

፹፭. ዳግመኛም እንዲህ አለ ፤ ‹‹በዝንጉዎች ምክር ያልሔደ ፣ በኃጥአን ጐዳናም ያልቆመ ፣ በዋ ዘኞች ወንበር ያልተቀመጠ ፣ ነገር ግን በእግዚአብሔር ሕግ፣ ደስ የሚለው ፣ ሕጉንም በሌ ሊትና በቀን የሚያስብ ሰው ምስጉን ነው::››

፹፮. አንተ ግን የክርስቲያን ማኅበርን ተውህ፤ የእግዚአብሔ ርንም ቤተ ክርስቲያን ናቅህ ፤ ሕጉንና ሥርዐቱንም አልጠበ ቅህም ፤ የወንበዴዎችንም ጐዳና ተከተልህ ፤ ርኩሱንም እንደ ንጹሕ አደረግህ::

፹፯. ከአንተ ከተለዩትም ጋራ ተወዳጀህ ፤ አኗኗርህንም ከአረ ማውያን ጋራ አድርገህ ፤ ርኵ ሰትንና ጥቅም የሌለው የብላሽ ነገርን ሁሉ የተመላ የዘፈን ቃልንም በጆሮህ ሰማህ::

፺፰. ወአንተሰ አበይከ ሰሚዐ ቃለ ኤርምያስ ነቢይ ዘይቤ እግዚኦ ኢነበርኩ ውስተ ዐውደ ምኑናን በዐመፃ አላ እፈርህ እምቅድመ ገጽከ[፲፯]፡

፺፱. በእንተ ምንት ትፈቅድ ትስማዕ ነገረ ምውታን አረማውያን እለ ቄስሉ በኀጢአት በምግባሩ ለዲያብሎስ እስመ ይቀትልዎ ለብእሲ ዘይተልዎሙ ፤ ወይመልህዎ እምርትዕት ሃይማኖት ፤ ወይሬስይዎ ይትቀነይ ለብዙኃን አማልክት ፤ ወአንትሙሰ ኢትግበሩ ከመዝ ፤ አላ ባሕቱ ዕቀቡ ትእዛዛቲሁ ለእግዚአብሔር ፤ ወኅረዩ ለክሙ ሕይወተ ፤ ወፈድፋደሰ ኅሡ ሕገ ቤተ ክርስቲያኑ ለእግዚአብሔር ።

፻. ወይእቲ እንተ አጥረያ በደሙ ክርስቶስ ፍቁር ወልድ ህልው እምቅድመ ይትፈጠር ዓለም፣ እስመ ይእቲ ቤተ ክርስቲያን ወለቱ ለልዑል ወእንተ ታጸንዕ አልባቢነ ፤ ወትሬስየነ ቅሩባነ ኀበ እግዚአብሔር ከመ ንርከብ ገጸ በኀቤሁ እስመ አባሉ ንሕነ ወአዕርክቲሁ።

፲፯ ኤር ፲፯ ፡ ፲፯

፺፰. አንተስ ‹‹አቤቱ በፍርድ አደባባይ በዐመፅ አልተቀመጥኩም፣ ነገር ግን ከፊትህ የተነሣ እፈራለሁ›› ያለውን የነቢዩን የኤርምያስን ቃል መስማትን አይሆንም አልህ።

፺፱. በዲያብሎስ ሥራ በኃጢአት የቄሰሉ የሙታን አረማውያን ነገርን ስለምን ትሰማለህ ? የሚከተላቸውን ሰው ይገድሉታልና ፤ ከቀናች ሃይማኖትም ይለዩታልና ፤ ለብዙዎች ጣዖታትም እንዲገዛ ያደርጉታልና ፤ እናንተ ግን እንደዚህ አታድርጉ ፤ ነገር ግን የእግዚአብሔርን ትእዛዞች ጠብቁ ፤ ለእናንተም ሕይወትን ምረጡ ፤ ይልቁንም የእግዚአብሔርን ቤተ ክርስቲያን ሕግ ፈልጉ ።

፻. ይህችውም ዓለም ሳይፈጠር በህልውና የነበረ ፣ የተወደደው እግዚአብሔር ወልድ ክርስቶስ በደሙ ገንዘብ ያደረጋት ናት፣ ይህችም ቤተ ክርስቲያን የልዑል ልጁ ናትና በእርሱ ዘንድም ባለ ሟልነትን እንድናገኝ የምታጸናንና ወደ እግዚአብሔር ቀራቢዎች የምታደርገን ናትና እኛ ወገኖቹና ወዳጆቹ ነንና።



፻፩. ንኩን እንከ ኄራነ ወንጹሓነ ዘእንበለ ርኩስ ፤ ወፍጹማነ በርትዕት ሃይማኖት ወበኵሉ ምግባረ ሠናይ።

## አንቀጽ ፲ወ፪

በእንተ ከመ ኢመፍትው ለክርስቲያን ይባኡ ውስተ ማኅደረ ነኪራን ሕዝብ ይርአዩ ተውኔተ ወማኅሌተ ይስምዑ።

፩. ተዐቀቡ እንከ እምዘ ከመዝ ግብር ወኢትደመሩ ውስተ ጉባኤ አሕዛብ።

፪. ወረኀቁ እመናግንቲሁ ለሰይጣን እስመ ለዲያሎብስ አልቦ ፍቅር ምስለ እግዚአብሔር እስመ ዘይዴመር ምስለ ዘይሄሊ ይግበር ሥምረቶ ለጸላዒ።

፫. ውእቱኬ ይትኌለቍ ምስለ ዲያብሎስ ፤ ወይወርስ መርገመ ረኀቁ እንከ እምግብር እኩይ እንተ አልባቲ ሠናይት።

፬. ዝውእቱ ተውኔት ፣ ወአምልኮ ጣዖት ፣ ወማርያን ፣ ወመዐስባን ወመሰግላን ፣ በአዕዋፍ ፣ ወመንቅሕያነ ምውታን ፣ እስመ ጽሑፍ ኢይኩን እኩይ ላዕለ ያዕቆብ ፣ ወኢሕሱም ላዕለ እስራኤል[፩]።

፩ ዘኍል ፳፫:፳፫

፻፩. እንግዲህ ያለርኵሰት ደጎችና ንጹሐን እንሁን ፣ በቀናች ሃይማኖትና በበጎ ምግባር ሁሉ ፍጹማን እንሁን ።

## ዐሥራ ሁለተኛ አንቀጽ

ክርስቲያኖች ጨዋታን ለማየትና ዘፈንን ለመስማት ወደ ልዩ ሕዝብ ማደሪያ ይገቡ ዘንድ እንዳይገባ ይናገራል።

፩. እንግዲህ እንዲህ ካለ ሥራ ተጠበቁ ፣ ወደ አሕዛብ ጉባኤም አትቀላቀሉ።

፪. ከሰይጣን አሽከላዎች ራቁ፣ ለዲያብሎስ ከእግዚአብሔር ጋር ፍቅር የለውምና፣የጠላትን ፈቃዱን ያደርግ ዘንድ ከሚያስብ ሰው ራቁ ።

፫. እርሱ ከዲያብሎስ ጋራ ይቈጠራልና ፤ እርግማንንም ይወርሳልና ፣ እንግዲህ በጎነት ከሌላት ከክፉ ሥራ ራቁ።

፬. ይኸውም መዝፈን ፣ ጣዖት ማምለክ ሟርተኞች ፣ ጠንቋዮች ፣ በወፍ የሚጠነቁሉ ፣ ሙት እናነሣለን የሚሉ ናቸው፣ ክፉ ነገር በያዕቆብ ላይ አይደረግ ፤ በእስራኤል ላይም መጥፎ ነገር አይሁን ተብሎ ተጽፎአልና።

፭. ሰስሉ እንከ እምዘ ከመዝ
ግብር ዘይገብሩ መጥዓውያን
ለአስሕቶ ሰብእ ዝውእቱ ምግ
ባራቲሁ ለሰይጣን።

፮. መፍትው ይትፌለጡ መሃ
ይምናን እማኅበረ ረሲዓን ወኢ
ይኅበሩ ገቢረ በዓል ምስሌ
ሆሙ ።

፯. ወከማሁ ንርኅቅ ንሕነሂ
እምኔሆሙ ወኢንባእ ውስተ
አብያቲሆሙ ወኢንብላዕ ምስሌ
ሆሙ ወኢንስተይ እስመ እሙ
ንቱ ፈጻምያነ ምግባራቲሁ
ለሰይጣን።

፰. ንትገኃሥ እምአምልኮ
ጣዖት ወስሕተት ወአምኃሆሙ
ወብፅዐተ አማልክቲሆሙ።

፱. ወአንትሙኒ ወራዙት ግበሩ
ኵሎ ትካዘ ዘይደሉ ለቅድስት
ቤተ ክርስቲያን ዘእንበለ ሀኬት
ወተሴሰዩ እምፍሬ ፃማክሙ
በንጽሕ ከመ ኢትጽሐቁ ወኢ
ምንተኒ።

፲. ወኢትክበዱ ዲበ ቤተ ክርስ
ቲያኑ ለእግዚአብሔር ከመ
ንኩን ዘእንበለ ትካዝ አላ
በስብከተ ወንጌል ቅዱስ።

፭. ሰውን ለማሳት ጣዖት
የሚያመልኩ ሰዎች ከሚያደር
ጉት ከእንደዚህ ያለ ሥራ
ራቁ፤ ይኸውም የሰይጣን ሥራ
ነው።

፮. ምእመናን ከክፉዎች ማኅ
በር ሊለዩ አገባብ ነው ፤ ከእ
ነርሱ ጋራም በዓልን በማድረግ
አንድ አይሁኑ።

፯. እኛም እንደዚሁ ከእነርሱ
እንራቅ ፣ ወደ ቤቶቻቸውም
አንግባ ፣ ከእነርሱ ጋራም አን
ብላ ፣ አንጠጣ ፣ እነርሱ የሰይ
ጣንን ሥራ የሚፈጽሙ ናቸ
ውና።

፰. ጣዖትን ከማምለክና ከስ
ሕተት ለጣዖታቱም አምኃ
ከመስጠትና ስለት ከመሳል
እንራቅ ።

፱. እናንተም ጐልማሶች የሚገ
ባውን ግዳጅ ሁሉ ያለ ሐኬት
ለቅድስት ቤተ ክርስቲያን አድ
ርጉ ፣ ምንም እንዳትቸገሩ በን
ጽሕና ከደከማችሁበት ፍሬ
ተመገቡ።

፲. ቅዱስ ወንጌልን በመስበክ
እንጂ ያለ ጭንቀት እንድንሆን
በእግዚአብሔር ቤተ ክርስቲያን
ላይ ሸክም አትሁኑ።



፲፩. ወኢናጽርዕ ቅኔ እደዊነ
ወኢንትሀከይ እስመ ቦ እምኔነ
መሠግራን ወቦ እምኔነ ሰፋ
ይያን ደብተራ ወቦ መስተገ
ብራነ ምድር።

፲፪. ይቤ ሰሎሞን ተመየጥ
ኀበ ቃሕም ኦ ሀካይ ወንቃሕ
ወቅናእ ርእየከ ፍናዊሁ ወኩን
ጠቢበ እምኔሁ።

፲፫. ወውእቱ እንዘ ወፍር
አልቦ ወዘሂ ያጌብሮ አልቦ
ወእንዘ እግዚእሂ አልቦ ያስተ
ጋብእ በሐጋይ ሲሳዮ ወብዙኀ
አመ ማእረር ይትጌበር አው
ሑር ኀበ ንህብ ወአእምር ከመ
መስተገብርት ይእቲ ወበ
ትግብርታ ከመ ሠናየ ትገብር
እንተ ፃማሃ ነገሥት ወአብዳን
ይነሥኡ ለሕይወት።

፲፬. እንተ ትትፌቀር ይእቲ
ኀበ ኵሉ ወክብርት ይእቲ
ወበኀይላ ፅብስት ወበግብራ
ጽንዕት ጥበበ አክቢራ አስተ
ርአየት።

፲፩. ተግባረ እድን አናቋርጥ ፣
ቸልም አንበል፣ ከእኛ ወገን ዓሣ
የሚያጠምዱ ከእኛም ወገን
ድንኳን የሚሰፉ ምድርንም የሚ
ያርሱ አሉና።

፲፪. ሰሎሞን እንዲህ አለ፣ አንተ
ታካች ወደ ግብረ ጉንዳን
ተመልከት ፣ ንቃ ጐዳናውንም
ተመልከተህ ከእርሱ ይልቅ
ጠቢብ ሁን።

፲፫. እርሱም መሰማሪያ ሳይ
ኖረው የሚያስገድደውም ሳይኖ
ረው ፣ ጌታም ሳይኖረው በበጋ
ምግቡን ይሰበስባልና ፣ በመኸ
ርም ጊዜ ብዙ ሥራ ይሠራልና፣
ወይም ወደ ንብ ሄደህ ሠራተኛ
እንደሆነች በሥራዋም መልካም
ሥራን እንደምትሠራ እወቅ ፣
የደከመችበትንም ሥራዋን ነገሥ
ትም ሰነፎችም ለመድኃኒት ይወ
ስዷሉና።

፲፬. ይህችም በሁሉ ዘንድ
የምትወደድ ናት ፣ የከበረችም
ናት፣ በኃይሏ ግን ደካማ ናት፣
ጥበብን አክብራ አሳየች።

፲፭. እስከ ማእዜኑ ኦ ሀካይ ትሰክብ፣ ወማዕዜኑ እምን ዋምከ ትነቅሕ፣ ሕቀ ትነውም ወሕቀ ትነብር፣ወሕቀ ትዴቅስ ወሕቀ ታስተጋብእ እዴከ ውስተ እንግድዓከ ፣ ወእምዝ ይመጽአከ ግብተ ከመ እኩይ ሐዋርያ ንዴት ወተፅናስ ከመ ኄር ረዋጺ ።

፲፮. ወእመሰ ኢኮንከ ሀካየ ይመጽእ ለከ ማእረርከ ከመ ነቅዐ ማይ ወንዴትሰ ከመ እኩይ ረዋጺ ለሲሁ ይርኅቅ እምኔከ።

፲፯. ብእሲ አብድ ወዐማፂ የሐውር ፍናዋተ ዘኢኮና ኄራተ[፬]።

፲፰. ወካዕበ ይቤ ዘይትጌበራ ለምድር ይጸግብ ኅብስተ።

፲፱. ወዓዲ ይቤ ኅብአ እዴሁ ሀካይ ውስተ ሕፅኑ ወየሐምም ለአቅርቦ ውስተ አፉሁ።

፳. ጠቢብ ያስተርኢ ለርእሱ ሀካየ ፣ አብድ ሐቀፈ እዴሁ ወበልዐ ሥጋሁ።

፬ ምሳ. ፮፡ ፲፪

፲፭. ሰነፍ ሆይ እስከ መቼ ትተኛለህ ? ከእንቅልፍህስ መቼ ትነቃለህ ? ጥቂት ትተኛለህ ፣ ጥቂትም ትቀመጣለህ፣ ጥቂትም ታንቀላፋለህ ፣ ጥቂት ጊዜም እጅህን ወደ ደረትህ ትሰበስባ ለህ ፤ ከዚህም በኋላ እንደ ክፉ መልእክተኛ ድህነት፣ እንደ ደገኛ ወ ራ ሪ ም ችጋር ፣ በድንገት ይመጣብሃል።

፲፮. ሰነፍ ባትሆን ግን መከር እንደ ውኃ ምንጭ ይመጣል ሃል ፣ ድህነት ግን እንደሚሸሽ ክፉ ወራሪ ከአንተ ይርቃል።

፲፯. ሰነፍና አላዋቂ በደለኛ ሰው በጎ ያይደሉ ጐዳናዎችን ይሄዳል።

፲፰. ሁለተኛም ምድርን የሚያ ርሳት እንጀራን ይጠግባል አለ።

፲፱. ዳግመኛም ሰነፍ ሰው እጁን ወደ ብብቱ ይሸሽጋል ፤ ወደ አፉ ለማቅረብም ይታመማል አለ ።

፳. ጥበበኛ ሰው ለራሱ አላዋቂ መስሎ ይታያል ፤ ሰነፍ ሰው እጁን አቅፎ ሥጋውን በላ አለ ።



፳፩. እስመ ግብሩ ለሀካይ አልባቲ ፈውስ።

፳፪. ኵሉ ዘኢይትቀነይ ኢይሴሰይ ወኢይንበር ምስሌክሙ ጽሩዐ[፫] ።

፳፫. ፍርሀዎኬ ኵሎ ጊዜ ወረ ኀቁ እምኀኬት እስመ እግዚአ ብሔር አምላክነ ይጸልእ ኵሎ ሀካያነ።

፳፬. ኢይንበር ሀካይ ምስለ እለ ይትኤዘዙ ለእግዚአብሔር አብ ዘሎቱ ክብር ወስብሐት ለዓ ለመ ዓለም አሜን።

## አንቀጽ ፲ወ፫

በእንተ መበለታት ዘአልቦን ምት፤

፩. መፍትው ትሠየም እንተ ፷ ክረምታ እንተ ባቲ ምግባረ ሠናይ።

፪. ኅሪት ወንጽሕት ዘኢትፈ ቅድ ዳግመ ብእሴ።

፫ ፩ኛ ተሰ. ፫፡፲-፲፫

፳፩. የሰነፍ ሰው ሥራ መድኃ ኒት የላትምና።

፳፪. ሥራ የማይሠራ ሁሉ ምግብን አይመገብ ፤ ሥራፈት ሆኖም ከእናንተ ጋራ አይቀመጥ።

፳፫. ሁለጊዜም ፍሩት ፤ ከስ ንፍናም ራቁ ፤ አምላካችን እግዚአብሔር ሰነፎችን ሁሉ ይጠላልና።

፳፬. ሰነፍ ሰው ከሚታዘዙ ሰዎች ጋራ አይቀመጥ ፣ ለእ ግዚአብሔር አብ ክብር ምስ ጋና ለዘለዓለሙ በእውነት ይግ ባው ። አሜን ።

## አሥራ ሦስተኛ አንቀጽ፣

ባል የሌላቸው የባልቴቶችን ነገር ይናገራል፤

፩. በጎ ምግባር ያላት ፣ ስልሳ ዓመት የሆናት ትሾም ዘንድ አግባብ ነው።

፪. ቸርና ከኃጢአት የነጻች ሁለተኛ ባል የማትሻ ልትሆን ይገባል።

፫. ለንዑሳትሰ መበለታት ኢይደልዎን ሢመት።

፬. ወእመሰ ሤምክሙ ነዐሰ መበለተ እንተ ኢትክል ተዐግሦ ከመ ልሂቃት መበለታት አላ ትፈቅድ ታውስብ ዳግመ ኢትእመንዋ።

፭. እስመ ታመጽእ ነገረ ኀፍረት ወኀሣረ ወነውረ ለቤተ ክርስቲያን ወትትኴነን በኀበ እግዚአብሔር እስመ አውሰበት ዳግመ ብእሴ ወኢዐቀበት ትእዛዘ መጻሕፍት።

፮. ወበእንተዝ ኢመፍትው ፍጡነ ይሢሙ ዘእንበለ ይሕትቱ ሕይወቶን ወያመክርዎን እመበን ትዕግሥት።

፯. ወእመሰ ኢይክህላ ተዐግሦ ይኄይስ ኢያንብቦቶን እስመ ኢዐቀባ ዘሰምዓ።

፰. ወእመሰበ ነአስ እንተ ነበረት ምስለ ምታ ኅዳጠ መዋዕለ ወተፈልጠት እምኔሁ በሞት ወእምዝ ሐይወት ባሕቲታ ወዐቀበት ግብረ መበለታት እንተ ከመዝ ትገብር ብፅዕት ይእቲ።

፫. ለታናናሽ መበለታት ግን ሹመት አይገባቸውም።

፬. እንደ ታላላቆች ባልቴቶች መታገሥ የማትችለውን በዕድሜ ትንሽ የሆነችውን መበለት ብትሾሙ ግን ዳግመኛ ታገባ ዘንድ ትሻለችና አትመኑአት።

፭. ለቤተ ክርስቲያን የኃፍረት ነገርን ውርደትንና ነውርን ታመጣለችና ሁለተኛም ባልን ስላገባች የመጻሕፍትንም ትእዛዝ ስለ አልጠበቀች በእግዚአብሔር ዘንድ ይፈረድባታልና።

፮. ስለዚህም አነዋወራቸውን ሳይመረምሩ ትዕግሥት እንዳላቸውም ሳይፈትኑ ፈጥነው ይሾሙ ዘንድ አግባብ አይደለም።

፯. መታገሥ ባይቻላቸው ግን አለማስተማር ይሻላል ፣ የሰሙትን አልጠበቁምና።

፰. ከባሏ ጋራ ጥቂት ቀን የኖረች፣ ከእርሱም በሞት የተለየች ፣ በዕድሜ ያነሰች መበለት ብትኖር ግን፣ከዚህ በኋላ እንዲህ እያደረገች የመበለታትን ሥራ ብትጠብቅና ብቻዋን ብትኖር ብፅዕት ናት።



፱. እንተ ተመሰለት ከመ መበለት እንተ ስራጵታ ዘሲዶና ዘመጽአ ኀቤሃ ወተወክፈቶ ለኤልያስ ነቢይ ቅዱሱ ለእግዚአብሔር።

፲. ወከመ ሐና ወለተ ፋኑኤል እንተ ነገደ አሴር እንተ ሐይወት ውስተ ቤተ እግዚአብሔር መዓልተ ወሌሊተ፣ ወድሉት ወትረ ለጸሎት ወአስተብቍዖት ወእንዘ ድንግል ይእቲ ነበረት ፲ወ፭ዓመተ ፣ ወምስለ ምታሰ ነበረት ፯ተ ዓመተ ፣ ወእምዝ ቦአት ውስተ ቤተ መቅደስ ወነበረት ወኮነት መዓስብተ ፹ወ፬ ዓመተ።

፲፩. ወትሴፎ ምጽአቶ ለክርስቶስ ወተአኵቶ ለእግዚአብሔር ወትዜኑ በእንቲአሁ ለኵሎሙ እለ ይሴፈዉ ምጽአቶ ለመድኃኒተ እስራኤል።

፲፪. ወዛቲ መበለት እንተ ትገብር ከመዝ ትረክብ ክብረ ወሞገሰ ወአኰቴተ በዝ ዓለም ወበከህክ በኀበ እግዚአብሔር በመንግሥተ ሰማያት።

፱. የእግዚአብሔር ቅዱስ ነቢዩ ኤልያስ ወደ እርስዋ እንደመጣና እንደ ተቀበለችው እንደ ሲዶና ስራጵታ መበለት የመሰለች።

፲. በመዓልትና በሌሊት በእግዚአብሔር ቤት እንደ ኖረች ከአሴር ወገን እንደ ሆነች እንደ ፋኑኤል ልጅ እንደ ሐና ለጸሎትና ለምልጃ ዘወትር እንደ ተዘጋጀች፣ በድንግልናም ዐሥራ አምስት ዓመት ኖረች፤ ከባሏም ጋር ሰባት ዓመት ኖረች ፤ ከዚህም በኋላ ወደ ቤተ መቅደስ ገብታ ፤ ሰማንያ አራት ዓመት መበለት ሁና ኖረች።

፲፩. የክርስቶስንም መምጣት ተስፋ ታደርግና እግዚአብሔርን ታመሰግን ነበር፣ እስራኤልንም ለማዳን መምጣቱን ተስፋ ለሚያደርጉ ሁሉ ስለ እርሱ ትናገር ነበር።

፲፪. እንደዚህ የምታደርግ ይህች ባልቴት በዚህ ዓለም በወዲያኛውም ክብርንና ሞገስን ምስጋናንም በእግዚአብሔር ዘንድ በመንግሥተ ሰማያት ታገኛለች።

፲፫. ወንዑሳት መበለታት ኢይሠየማ በውስተ ቤተ ክር ስቲያን እስመ ኢይክላ ተዐግሦ ስብሳብ እንዘ ሀለዋ በኀይለ ውርዙቶን እስመ ያወስባ ዳግመ ብእሴ።

፲፬. ወለእማንቱሰ ይከውን ውርዙቶን ለሰይጣን ፤ አላ ባሕቱ ይትዓቀባ ወያድኅና ርእሶን ከመ ኢያውስባ ዳግመ ብእሴ።

፲፭. መፍትው ለክሙ ትለ ብዉ ዘንተ ከመ ዝንቱ ቀዳ ማዊ ስብሳብ ንጹሕ በኀበ እግዚአብሔር ።

፲፮. ወእለሰ ያወስቡ ዳግመ ይከውኑ ውፁኣነ እምሕግ እስመ ኢኮነ ባሕቲቱ በእንተ ሩካቤ አላ ሐሰዉ ላዕለ እግዚ አብሔር።

፲፯. ወእለሰ ያወስቡ ሣልሰ ኢይትኌለቁ ውስተ መርዔቱ ለእግዚአብሔር።

፲፰. ወእለሰ ያወስቡ ራብዐ ፈድፋደ ተዐውቀ ዝሙቶሙ፣ ወይረክቡ ኀፍረተ ወኀሣረ።

፲፫. ሕፃናት ሴቶች ግን በቤተ ክርስቲያን ውስጥ አይሾሙ ፤ የፈቲውን ፆር መታገሥ አይቻ ላቸውምና ፤ በወጣትነት ኀይል ዳግመኛ ወንድን ያገባሉና።

፲፬. የእነርሱ ግን ቍንጅናቸው ለሰይጣን ይሆናል ፤ ነገር ግን ራሳቸውንም ያድኑ፣ ይጠብቁ፣ ዳግመኛ ወንድን እንዳያገቡ።

፲፭. መጀመሪያው ጋብቻ በእግ ዚአብሔር ዘንድ የአማረ ንጹሕ እንደሆነ ይህን ታስተውሉ ዘንድ ለናንተ አገባብ ነው።

፲፮. ሁለተኛ የሚያገቡ ግን ከሕግ የወጡ ይሆናሉ ፤ በእግዚአብሔርም ላይ ሐሰትን ተናገሩ እንጂ ስለ ጋብቻ ብቻ አይደለምና።

፲፯. ሦስተኛ የሚያገቡ ግን ከእግዚአብሔር መንጋ ከምዕ መናን አይቈጠሩም።

፲፰. አራተኛ የሚያገቡ ግን መሰ ሰናቸው ፈጽሞ ታወቀ፣ ኀፍረት ንና ውርደትን ያገኛሉ።



፲፱. እስመ በቀዳሚ ፍጥረት ወሀበ እግዚአብሔር አሐተ ብእሲተ ለአሐዱ ብእሲ፣ ወበእ ንተዝ ይከውኑ ፪ኤሆሙ ፩ ሥጋ።

፳. ከመዝ ንኤዝዝ ለውር ዝዋት አንስት እምከመ ሞቱ ዘቀዳሚ አምታቲሆን እምከመ ኢይክላ ተዓግሦ መፍትው ያውስባ ዳግመ ብእሴ ከመ ኢይደቃ ዳግመ ውስተ መሥ ገርተ ሰይጣን እኩይ ወመ ናግንቲሁ ማህጕሌ ነፍሳት።

፳፩. ወእማንቱሰ ይወርዳ ውስተ ኵነኔ ገሃነም ዘለዓለም ዘአልቦ ዕረፍት።

፳፪. ወመበለታት እለ ተዐውቃ በጽድቅ አንስትኒ እለ አውሰባ ፩ ብእሴ ወብዙኃን ሰማዕት ኮኑ በእንቲአሆን ከመ ሐይዋ በንጽሕ ወእማንቱኬ ኢይት ኌለቋ ምስለ መበለታት ካል ኣት ወየሐፅና ደቂቆን ዘእ ንበለ ርኵስ ፣ ለእለ ከመዝ መፍትው ትርድእዎን ወተሀብ ዎን ትካዞን እስመ እማንቱ ትውክልቶን ኀበ እግዚአብ ሔር ።

፲፱. በመጀመሪያው ፍጥረት እግዚአብሔር አንዲት ሴትን ለአንድ ወንድ ሰጥቷልና ፣ ስለ ዚህም ሁለቱ አንድ አካል ይሆ ናሉ ።

፳. ለቆነጃጅቶች ሴቶችም የቀ ድሞ ባሎቻቸው ከሞቱባቸው መታገሥ ባይቻላቸው ሁለተኛ ባል ያገቡ ዘንድ እንዲገባ እናዛለን ፣ ወደ ክፉ የሰይጣን ወጥመድ ነፍሳትንም ወደሚያ ጠፋ አሽክላው ዳግመኛ እንዳ ይወድቁ።

፳፩. እነርሱ ግን ለዘለዓለሙ ዕረፍት ወደሌለበት ወደ ገሃነም ይወርዳሉ።

፳፪. በጽድቅ የታወቁ ባልቴቶች አንድ ባል ያገቡ ሴቶች በንጽሕና እንደኖሩ ብዙ ሰዎች ምስክርን የሆኗቸው እነዚህም ከሌሎች ባልቴቶች ጋራ አይቆጠሩም ፣ ልጆቻቸውንም ያለ ርኵሰት ያሳደጉ እንደእነዚህ ያሉትን ትረ ዷቸውና ግዳጃቸውን ትሰጧቸው ዘንድ አግባብ ነው ፤ የእነዚህ እምነታቸው በእግዚአብሔር ዘንድ ነውና።

፳፫. ወይእዜኒ ኤጲስ ቆጶስ ስፋሕ እዴከ ለውሂብ ወተዘከ ሮሙ ለነዳያን ወሀብ ለለ፩፩ ጸሕቆሙ በከመ ይፈቅዱ ወሐ ውጾሙ ለዕቤራት ወለዕጓለ ማውታ ወለምንዱባን ፡፡

፳፬. መፍትው ኤጲስ ቆጶስ ይርድኦሙ ወያድኅኖሙ ወየ ሀቦሙ ትካዞሙ ለኵሎሙ ፅኑሳን ወጽዑራን፡፡

፳፭. ወይርድኦሙ ወይርዐ ዮሙ ለኵሎሙ ሕዝብ ውስተ ሠናይ መርዔት ለእለ ያቄርቡ ጽርስፎራ፡፡

፳፮. ምጽዋተ እምዘ አብኡ ለከ ጸጉ ዘአምጽኡ ኅቤከ ለለ፩፩ በከመ ይደሉ ከመ መጋቢ ኄር ወመሓሪ እስመ ሥሙር ውእቱ በኅበ እግዚአብሔር፡፡

፳፯. ኵሉ ዘይጼጉ ለጽኑሳን ይረክብ ዐስበ ሠናየ፡፡

፳፰. ወአንተሰ ዓመውከ በእንተ እግዚአብሔር ትነሥእ ዕሤተ፡፡

፳፱. ወከመዝ በሎሙ ለእለ ጸገውከ ዕገሌ ዘአቅረበ ወሀብኩ ክሙ ከመ ትጸልዩ ሎቱ ወታስተብቍዑ በእንቲአሁ፡፡

፳፫. ዛሬም ኤጲስ ቆጶስ ሆይ ! ለመስጠት እጅህን ዘርጋ ፤ ድሆችንም አስባቸው ፤ ለእያ ንዳንዳቸው ግዳጃቸውን እንደ ሚሹት ስጥ ፤ ባልቴቶችንም እናት አባታቸው የሞቱባቸው ንም፤ችግረኞችንም ጉብኛቸው ፡፡

፳፬. ኤጲስ ቆጶስ የተቸገሩትንና የተጨነቁትን ሁሉ ሊረዳቸውና ሊአድናቸውም ግዳጃቸውን ሊሰ ጣቸው አገባብ ነው፡፡

፳፭. በመልካም መንጋ መካከል መባ የሚያቀርቡትን ሕዝቡንም ሁሉ ይርዳቸው ፤ ይጠብቃ ቸው፡፡

፳፮. ለአንተ ከአገቡት ምጽ ዋትም፤ ወደ አንተ ያመጡልህን እንደቸርና አዛኝ ሹም ለየአንዳ ንዱ እንደሚገባ ስጥ ፤ ይህ በእግዚአብሔር ዘንድ የተወደደ ነውና፡፡

፳፯. ለተቸገሩ የሚሰጥ ሁሉ በጎ ዋጋን ያገኛል ፡፡

፳፰. ስለ እግዚአብሔር የደከ ምክ አንተም ዋጋህን ታገኛለህ፡፡

፳፱. ለምትሰጣቸውም ሰዎች ‹‹ትጸልዩለትና ስለ እርሱም ትማልዱ ዘንድ›› ዕገሌ ያቀረበ ውን ሰጧዋችሁ በላቸው ፡፡



፴. መፍትው ሠናየ ትግበሩ ለኵሉ ሰብእ ወኢትበሉ ለዝ እሁቦ ወለካልኡ እከልዮ፡፡

፴፩. ወአንተሰ ኤጲስ ቆጶስ ኢትፍልጥ ወኢመነሂ እስመ ይቤ እግዚእነ ለኵሉ ዘሰአለከ ሀቦ[1] ዝውእቱ እመኒ ዐርክከ፤ ወእመኒ ጸላኢከ ፤ ወለእመኒ ዘመድከ ፤ አው ፈላሲ አው ዘአውሰበ አው ዘአልቦ ብእ ሲት አው መበለት አው ዕጓለ ማውታ ወለኵሉ ግብር ሠናየ፡፡

፴፪. እስመ አዘዘነ እግዚእነ በውስተ መጻሕፍት ንምሐ ሮሙ ለነዳያን፡፡

፴፫. በከመ ይቤ በኢሳይያስ ነቢይ ፈትት ኅብስተከ ለር ኁብ ፤ ወአብልዖ ለነዳይ ፤ ወአኅድሮ ውስተ ጽላሎተ ቤትከ፡፡

፴፬. ወእመ ርኢከ ዕሩቀ አልብሶ ወኢትትአወር እምዘ ርዐ ቤትከ[2]፡፡

፴፭. ወዳንኤልኒ ይቤ በእንተዝ ያሠምርከ ምክርየ ኦ ንጉሥ ወበምጽዋተ ጽድቅ ትድኅን፡፡

፴. ለሰው ሁሉ በጎ ነገርን ታደርጉ ዘንድ ይገባል ፤ ለዚህ እሰጠዋለሁ ፤ ሌላውን እከለክ ለዋሁ አትበሉ፡፡

፴፩. አንተም ኤጲስ ቆጶስ ማን ንም አትለይ፤ ጌታችን ለለመ ነህ ሁሉ ስጠው ብሏልና፤ ይህ ንም ማለት ወዳጅህም ቢሆን፤ ጠላትህም ቢሆን፤ ዘመድህም ቢሆን፤ ወይም ስደተኛ ቢሆን፤ ወይም ያገባ ቢሆን፤ ሚስት የሌለውም ቢሆን ፤ ባል የሌላ ትም ብትሆን እናት አባት የሞቱ በትም ቢሆን ፤ ለሁሉም በጎ ነገርን አድርግ፡፡

፴፪. ጌታችን ለችግረኞች እን ራራላቸው ዘንድ በመጻሕፍት አዝዞናልና፡፡

፴፫. በነቢዩ በኢሳይያስ እን ጀራህን ለተራበ ቍረስ ፤ ለድኃ ውም አብላው ፤ በቤትህ ጥላ ውስጥም አሳድረው እንዳለ፡፡

፴፬. የታረዘንም ብታይ አል ብሰው፤ የሥጋ ዘመድህንም ችል አትበል፡፡

፴፭. ዳንኤልም ንጉሥ ሆይ ስለዚህ ነገር ምክሬ ደስ ያሰኝህ በእውነተኛ ምጽዋት ትድናለህ አለ ፡፡

[1] ማቴ ፭ ፥ ፵፪

[2] ኢሳ ፶፰ - ፯

፴፮. ወኀጢአትከኒ በምሒረ ነዳያን ይሠረይ ለከ እስከ ይሠሪ ጌጋየከ እግዚአብሔር[፫]::
፴፯. ወካዕበ ይቤ ሰሎሞን እስመ በአሚን ወበምሂር ይደመሰስ ኀጢአት::

፴፰. ወዓዲ ይቤ ዳዊት ብፁዕ ዘይሌቡ ላዕለ ነዳይ ወምስኪን እምዕለት እኪት ያድኅኖ እግዚ አብሔር[፬]:

፴፱. ወካዕበ ይቤ ዘረወ ወወ ሀበ ለነዳይ ወጽድቁኒ ይነብር ለዓለም[፭]::
፵. ወካዕበ ይቤ ሰሎሞን ዘይምሕሮ ለነዳይ ይሌቅሖ ለእግዚአብሔር ወይትዐሠይ በከመ ወሀበ ::
፵፩. እስመ ዘያጸምም እዘኒሁ ከመ ኢይስማዕ አውያተ ነዳይ፣ ዘይከድን ዓይኖ ከመ ኢይርአይ ግፉዐ ፣ ሎቱኒ ይጸመሞ እግዚአብሔር::

፫ ዳንኤ ፬ ፡ ፳፬
፬ መዝ. ፵፱ - ፩ - ፪
፭ መዝ. ፻፲፩ - ፱

፴፮. እግዚአብሔር በደልህን እስቲያቀልልህ ድረስ ኃጢአትህ ነዳያንን በመመጽወት ይሠረ ይልሃል አለ::
፴፯. ሁለተኛም ሰሎሞን በሃይ ማኖትና በመራራት ኃጢአት ይደመሰሳል አለ::

፴፰. ዳግመኛም ዳዊት ለችግረ ኛውና ለምስኪን የሚያስብ ብፁዕ ነው፤ እግዚአብሔር ከክፉ ቀን ያድነዋል አለ::

፴፱. ሁለተኛም ገንዘቡን በተነ ፣ ለደኃም ሰጠ ፣ ጽድቁም ለዘለ ዓለም ይኖራል አለ::
፵. ዳግመኛም ሰሎሞን ለድኃ የሚራራ ለእግዚአብሔር ያበድ ራል እንደሰጠም ይቀበላል::

፵፩. የድኃውን ጩኸት እንዳ ይሰማ ጆሮውን የሚደፍን ፣ የተገፋውንም እንዳያይ ዓይኑን የሚከድን ፣ እሱንም እግዚአ ብሔር ቸል ይለዋል::



፵፪. መፍትው መበለታት ይኩና ዕጉሣተ እለ ኢያበዝኃ ነቢበ ወአልቦን እከይ ወኢመዓት::

፵፫. አላ እማንቱ ንጹሓት ወያመልካሁ ለእግዚአብሔር በጽድቅ::

፵፬. ወእምከመ ርእያ እኩየ ምግባረ ወሕሡመ ቃለ ያር ምማ ከመ ዘኢርእያ ወኢሰ ምዓ::

፵፭. ወኢይኩን ትካዛ ለመ በለት ወኢምንትኒ ዘእንበለ ጸልዮ ወአስተብቍዖ በእንተ እለ ይመጽኡ ወያበውኡ መባአ ለቤተ ክርስቲያን::
፵፮. ወእመሰቦ ዘየኃሥሥ ጽሩዐ ነገረ ከንቱ ኢያውሥ አሁ ፣ አላ ባሕቱ ይትወከፋ ለእለ የኀሥሣ ቃለ ሃይማኖት ወምግባረ ጽድቅ ፣ ወይሣተፋ ሠናየ በኀበ እግዚአብሔር::

፵፯. ወእለሰ ይፈቅዳ ይትመ ሀራ ሥርዐተ ይሑራ ኀበ ሥዩማን ወይትመሐራ ወይስ ምዓ ቃለ ተግሣጽ::

፵፪. ባልቴቶች ትዕግሥተኞች ነገርን የማያበዙ፣ ክፋትና ቊጣ የሌለባቸው ይሆኑ ዘንድ አገባብ ነው::

፵፫. ነገር ግን እነሱ ንጹሖች እግዚአብሔርን በእውነት የሚ ያመልኩት ይሁኑ::

፵፬. ክፉ ሥራን ቢያዩ ፣ ክፉ ቃልንም ቢሰሙ ፣ እንዳላዩና እንዳ ልሰሙ ዝም ይበሉ ::

፵፭. የባልቴት አሳቧ ለቤተ ክርስቲያን መባ ለማግባት ስለሚ መጡት ከመጸለይና ከመማለድ በቀር ሌላ ምንም አይሁን::

፵፮. የተጠላ ከንቱ ነገርን የሚሻ ሰው ቢኖር አይመልሱለት ነገር ግን የሃይማኖትን ቃልና የጽድቅ ሥራን የሚፈልጉትን ይቀበሉ ፣ በእግዚአብሔር ዘንድም በጐ ነገርን ይሳተፉ ::

፵፯. ሥራትን ይማሩ ዘንድ የሚሹ ወደ መምህራን ሄደው ይማሩ የምክር ቃልንም ይስሙ ::

፵፰. ወኢይስምዓ ቃለ ውዴት ወኢይትልዋ ድኅረ ባዕዳነ አማልክት አላ ያምልካሁ ለ፩ እግዚአብሔር ዘፈጠረ ኵሎ።

፵፱. እስመ አስተማሰላ እግዚአብሔር ለመንግሥተ ሰማያት በኅጠተ ሰናፔ እንተ ትንዕስ እምኵሉ አዝርዕት[፯] ወሶበ ጥዕማ ብእሲ ታውዕዮ ከማሁ ውእቱ ቃለ ትምህርተ ሃይማኖት ታውእዮ ለሰይጣን።

፶. ኢመፍትው ንዕሉ ቃለ ነቢያት ወኢንክሥት ምሥጢረ ለዕልዋነ ሃይማኖት።

፶፩. አላ ንጽናዕ በሃይማኖት እስመ አዘዘነ እግዚእነ እንዘ ይብል ኢትደዩ ባሕርየክሙ ቅድመ አሕርው ወኢትሀቡ ቅድሳቲክሙ ለከለባት ከመ ኢይኪዱ ባሕርየክሙ በእገሪሆሙ ወተመዪጦሙ ይነጽሑክሙ እስመ ሶበ አእመሩ ነገረ ምሥጢር ዕልዋን ይሜንኑ ወይሬስዩ ኀፍረተ ወኀሣረ በዕበዶሙ።

፶፪. አላ ዳዕሙ መሀርዎሙ ይለብዉ ቃለ ኦሪት ወነቢያት እለ ተነበዩ በእንተ ምጽአቱ ለክርስቶስ።

፶፫. እስመ መምህርነ ኢየሱስ ክርስቶስ ፈነወ ለነ ፲ወ፪ተ ሐዋርያተ ንምሀሮሙ ለኵሎሙ አሕዛብ።

፶፬. ወለአንስትሰ ኢአዘዘን ይምሀራ ወያንብባ በቤተ ክርስቲያን ላዕለ ሕዝብ አላ ዳዕሙ ይትገሠሣ እምግብረ ዝሙት ወይትአዘዛ በጾም ወበጸሎት ወበአጽምዖ ቃለ መጻሕፍት።

፯. ማቴ. ፲፫. ፴፩–፴፪

፵፰. የነገር ሥራ ቃልን አይስሙ፣ ልዩዎች አማልክትንም አይከተሉ፣ ሁሉን የፈጠረ አንድ እግዚአብሔርን ያምልኩት እንጂ።

፵፱. እግዚአብሔር መንግሥተ ሰማያትን ከአዝርእት ሁሉ በምታንስ በሰናፍጭ ቅንጣት መስሏታልና፣ ሰው በቀመሳት ጊዜ ታቃጥለዋለች፤ የሃይማኖት ትምህርት ቃል እንዲሁ ናት፣ ሰይጣንን ታቃጥለዋለችና።

፶. የነቢያት ቃልን እንወነጅል ዘንድ አይገባም፤ ሃይማኖትን ለካዱ ሰዎችም ምሥጢርን አንግለጽ።

፶፩. ነገር ግን በሃይማኖት እንጽና፣ "ጌታችን ዕንቈቻችሁን በእሪያዎች ፊት አትጣሉ፤ የተቀደሰውንም ለውሾች አትስጡ፤ ዕንቈቻችሁን በእግራቸው እንዳይጠቀጥቁት፣ ተመልሰውም ይጥሏችኋል" ብሎ አዝዞናልና፣ከሐድያን በስንፍናቸው የምሥጢርን ነገር ባወቁ ጊዜ ይንቃሉ፤ ኀፍረትና ውርደትንም ያደርጋሉ።

፶፪. ነገር ግን የኦሪትንና ስለ ክርስቶስ መምጣት ትንቢት የተናገሩ የነቢያትን ቃል ያስተውሉ ዘንድ አስተምሯቸው እንጂ።

፶፫. መምህራችን ኢየሱስ ክርስቶስ አሕዛብን ሁሉ እናስተምር ዘንድ እኛን አስራሁለቱ ሐዋርያትን ልኮልናልና።

፶፬. ሴቶችን ግን ሊያስተምሩ በቤተ ክርስቲያንም ለሕዝቡ ሊያነብቡ አላዘዛቸውም፤ ከመሰሰን ሥራ ይገሥፁ፤ በጾም፣ በጸሎትና የመጻሕፍትን ቃል በማድመጥ ይታዘዙ ዘንድ ነው እንጂ።



፶፭. እስመ ነበራ ምስሌነ ማርያም መግደላዊት ወአኅቲሁ ለአልዓዛር ማርያ ወማርታ ወሰሎሜ ወባዕዳትሂ እለ ምስሌሆን እስመ ለእሉን ኢአዘዞን ይምሐራ ምስሌነ።[፯]

፶፮. ወባሕቱ መፍትው ይምሀራ ለአንስት።

፶፯. እስመ ብእሲ ርእሳ ለብእሲት ከማሁ ኢመፍትው ወኢርቱዕ ይኩን አባል ዘየዓቢ እምርእስ።

፶፰. ኢመፍትውኬ መበለታት ወደናግል ያንሶስዋ ማዕከለ መራህብት ወይባኣ ቤተ ዕደው።

፶፱. ወእለሰ ይገብራ ከመዝ ኢኮና መበለታተ ወኢደናግለ አላ ዳዕሙ ይከውና ማዕቀፈ ለሰብእ።

፷. ወእመሰ ኢይፀመዳ ውስተ ቤተ ክርስቲያን ይከውና ሀካያተ ወስሱዓተ ወኀሣሥያተ ንዋየ ባዕድ ወይጼውዋ ዕደወ ወይከውና መስሕታተ ለካልኣን ወያወድቃ ነፍሳተ።

፷፩. ወእለሰ ይተልውዎን ይርኅቁ እምእግዚአብሔር ።

፷፪. ወእለሰ ይበውኡ ውስተ ቤተ ክርስቲያን ወኢይሌብዉ ዘውስተ መጻሕፍት ወኢይሰምዑ ቃለ መጽሐፍ ዘተግሣጽ በእንተ እለ ይገብሩ ከመዝ ይቤ ኢሳይያስ ነቢይ ሰሚዐ ይሰምዑ ወኢይሌብዉ።[፰]

[illegible]
፰ ኢሳ ፮ : ፱

፶፭. ማርያም መግደላዊትና የአልዓዛር እኅቶች ማርያና ማርታ ሰሎሜም ሌሎችም ከእነርሱ ጋራ የነበሩ ሴቶች ከእኛ ጋራ ነበሩ፤ እነርሱን ከእኛ ጋራ ያስተምሩ ዘንድ አላዘዛቸውምና።

፶፮. ነገር ግን ሴቶችን ያስተምሩ ዘንድ ይገባል።

፶፯. ወንድ ለሴት ራስዋ ነውና እንደዚሁ አካል ከራስ የበለጠ ይሆን ዘንድ አይገባም።

፶፰. ባልቴቶችና ደናግል በአደባባይ መካከል ሊመላለሱና ወደ ወንዶች ቤትም ሊገቡ አይገባም።

፶፱. እንደዚህ የሚያደርጉ ግን ባልቴቶችና ደናግል አይደሉም ለሰው መሰናክል ይሆናሉ እንጂ።

፷. በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ባያገለግሉ ግን ሰነፎች ስሱዎችና የሰው ገንዘብ ፈላጊዎች ይሆናሉ፣ ወንዶችንም ይማርካሉ፣ ለሌሎችም መሳሳቻ ይሆናሉ፣ ነፍሳትንም ይጥላሉ።

፷፩. የሚከተሏቸውም ከእግዚአብሔር ይርቃሉ።

፷፪. ወደ ቤተ ክርስቲያን ገብተው በመጻሕፍት ያለውን ስለማያስተውሉ የተግሣጽ መጽሐፍ ቃልንም ስለማይሰሙ እንዲህ ስለሚያደርጉ ሰዎችም ነቢዩ ኢሳይያስ እንዲህ ይላል ፣ መስማትን ይሰማሉ አያስተውሉም እንጂ ።

፳፫. ወራእየ ይሬእዩ ወኢይጤይቁ በከመ ጽሉል ልቦሙ ለዝንቱ ሕዝብ ወለእለሰ ከመዝ መበለታት ኢታርእይዎን መሥዋዕቶ ለክርስቶስ።

፳፬. ወእንተሰ ትፈቅድ ታሥምሮ ለክርስቶስ ትንበር ውስተ ቤታ በጽምው፣ ወትሰብሖ መዓልተ ወሌሊተ በአፍ ዘኢያረምም፣ ወትስአሎ ለእግዚአብሔር በልብ ንጹሕ ከመ ጠባብ ዮዲት እንተ ሰአለት ኀበ እግዚአብሔር መዓልተ ወሌሊተ በእንተ እስራኤል።[9]

፳፭. ከማሁ መበለት መሐሪት ትስአሎ ለእግዚአብሔር እንዘ ኢታጸርዕ ሐዊረ ቤተ ክርስቲያን በኵሉ ሰዓት ።

፳፮. እስመ ኵሉ ሕሊናሃ ድልው ወትረ ለተቀንዮ ወኢትትመየጥ ውስተ ፍግዕ።

፳፯. ወእንተሰ ንጹሕ አዕይንቲሃ ወቅዱስ እዘኒሃ ወኢትስፍሕ እደዊሃ ኀበ ትዕግልት ወይረውጻ እገሪሃ ውስተ ፍኖተ ሰላም ወአፉሃ ኢይነብብ ሐሰተ ወሲሳያ በዐቅም ለእንተ ከመዝ ምግባራ ይሰምዓ እግዚአብሔር ጸሎታ ወስእለታ።

፳፫. ማየትንም ያያሉ አይረዱም እንጂ፣ ይህ ሕዝብ ልቡ ደንድኗል፣ እንደነዚህ ላሉት መበለታት የክርስቶስን መሥዋዕት አታሳዩአቸው።

፳፬. ክርስቶስን ደስ ልታሰኘው የምትወድ ግን በቤቷ በጸጥታ ትኑር፣ ዝም በማይል አፍም ሌሊትና ቀን ታመስግነው፣ ስለ እስራኤል ሌሊትና ቀን ወደ እግዚአብሔር እንደ ለመነች እንደ ጥበበኛዋ ዮዲትም በንጹሕ ልብ እግዚአብሔርን ትለምነው።

፳፭. እንደዚሁ የምትራራ ባልቴት በየሰዓቱ ቤተ ክርስቲያን መሄድን ሳታቋርጥ እግዚአብሔርን ትለምነው።

፳፮. ሐሳቧ ሁሉ ለመገዛት የተዘጋጀ ነው፤ ወደ ተድላ ደስታ አትመለስምና።

፳፯. ዓይኖቿ ንጹሕ፣ ጆሮቿ ቅዱስ የሆኑ፣ እጆቿን ወደቅሚያ የማትዘረጋ፣ እግሯም ወደሰላም መንገድ የሚሮጥ፣ አፏም ሐሰትን የማይናገር፣ ምግቧም በልክ የሚሆን፣ ምግባሯ እንደዚህ የሆነውን ሴት እግዚአብሔር ልመናዋንና ጸሎትዋን ይሰማታል።

---

[9]. ዮዲት. ፱ ፡ ፩



፳፰. እስመ ይቤ አመ ዕለተ እጼውዐከ ፍጡነ ስምዓኒ።[10]

፳፱. ወከመዝ ትሠየም መበለት እንተ ኢታፈቅር ወርቀ ወአልባሰ ትዝኅርት ወኢስስዕት ወኢመስተራብሒት።

፴. አላ ዳዕሙ ኅሪት ወለባዊት ወትንበር ውስተ ቤተ ክርስቲያን እንዘ ትሴብሕ ወትዜምር ወታነብብ መጻሕፍተ ወተዐቅብ ጊዜ ሰዓተ መዓልት ወሌሊት ወትጸውም ወትስአሎ ለእግዚአብሔር ኵሎ ጊዜ።

፴፩. ወቅኔ እደዊሃ ትሁብ ለነዳያን ወኢታጥሪ ኢምንተኒ።

፴፪. እንዘ ትዜክር መበለተ እንተ አብአት ፪ተ ጸራይቀ ውስተ ቤተ መቅደሱ ለእግዚአብሔር ዘበእንቲአሃ ስምዐ ኮነ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ በውስተ ወንጌል አማን እብለክሙ ከመ ዛቲ መበለት አብዝኀት አብአ እምኵሎሙ እለ አብኡ ውስተ ሙዳየ ምጽዋት ወኵሎሙ እለ አብኡ እምተረፈሙ አብኡ።

፴፫. ወይእቲሰ እምተጽናሳ ኵሎ ዘባቲ አብአት ወኵሎ መንበርታ።

፴፬. መፍትወኬ መበለታት ይኩና ንጹሓተ ወይትሓታ በፍርሀት ወበረዓድ።

፳፰. በምጠራህ ጊዜ ፈጥነህ ስማኝ ይላልና።

፳፱. እንደዚህም ወርቅ የማትወድ፣ ትዕቢትና ስስት የሌላት፣ ገንዘብ የማታራባ ባልቴት ትሾም።

፴. ነገር ግን ቸር አስተዋይ ትሁን፣ በቤተ ክርስቲያን ውስጥም እያመሰገነች፣ እየዘመረች፣ መጻሕፍትን እያነበበች፣ የሌሊቱንና የቀኑንም ሰዓት ጊዜ እየጠበቀች፣ እየጾመች፣ ሁልጊዜም እግዚአብሔርን እየለመነች ትኑር።

፴፩. ከእጆቿ ሥራም ለነዳያን ትስጥ፣ ምንም ጥሪት አታኑር።

፴፪. በእግዚአብሔር ማደሪያ በቤተ መቅደስ ሁለት እንጀራ ያቀረበችውን ድኃ እያሰበች፤ ስለ እርሷ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በወንጌል እንዲህ ብሎ ምስክር የሆናት፣ በሙዳየ ምጽዋቱ ውስጥ መባዓቸውን ከአገቡት ሁሉ ይልቅ ይች ድኃ መባ መስጠትን እንዳበዛች በእውነት እነግራችኋለሁ፣ ሁሉም ያገቡት ከትርፋቸው ነውና።

፴፫. ይቺ ግን ችግረኛ ስትሆን ያላትን ንብረቷን ሁሉ አገባች።

፴፬. ባልቴቶች ንጹሖች ይሆኑ ዘንድ በመፍራትና በመንቀጥቀጥም ትሕትናን ያደርጉ ዘንድ አገባብ ነው ።

---

[10]. [illegible]

፸፫. ወፈድፋደሰ ለኤጲስ ቆጶስ ወለቀሳውስት ወለዲያቆናት ወለ ዲያቆናዊት::

፸፬. ወእማንቱሰ ኢይግበራ ወኢም ንተኒ ዘእንበለ ምክረ ዲያቆናት::

፸፭. ወኢይሑራ ውስተ ሐውዘ መባ ልዕት ወንዝህላል::

፸፮. እመሰ ተረክባ እንዘ ከመዝ ይገብራ ይትገሠጻ ይትነሣእ ዲያ ቆን ወየአዝዞን ይጹማ::

፸፯. ወከማሁ ካህናትኒ እመ ይነ ሥኡ ርዴ በኀበ መሰጥ ወመወ ልጣን ወዘማውያን ይትገሠጹ ወኢ.ታብእ ቊርባነ ለእግዚአብሔር አምላክከ::

፹. ወመፍትውኬ ይኩና መበለታት ድልዋተ ለሰሚዐ ቃለ መላህቅቶን ወይግበራ ኵሎ ዘየአዝዝዎን ወይ ዕቀባ ቃለ ኤጲስ ቆጶስ ወያክብራሁ ከመ ዘእግዚአብሔር::

፹፩. ወእመሰቦ ዘይነሥእ ምጽዋተ እምኀበ ዐማፅያን ወዕልዋን ይድ ኀፅ ውስተ ስሕተት ዘዚአሆሙ ወይመውት በጌጋዮሙ ወለእመ ጸለየ በእንቲአሆሙ የኀዝና ለክርስቶስ::

፹፪. ወባሕቱ ይሚጦሙ ውስተ ንስሓ::

፹፫. ወእመሰ ጸለየ ወይቤ አድኀን እለ ኢ.ተመይጡ ውስተ ንስሓ ዓማ ፅያነ ወሐሳውያነ ወኃጥአነ ይትካ ፈል እከየ ምግባሮሙ ለእሉ::

፸፫. ይልቁንም ለኤጲስ ቆጶስ፣ ለቀ ሳውስት፣ ለዲያቆናትና ለዲያቆና ዊት::

፸፬. እነዚህ ግን ያለዲያቆናት ምክር ምንም አያድርጉ::

፸፭. የመብል ጣዕም ማሻሻል፣ አለል ዘለል ማለት ወደ አለበት አይሒዱ::

፸፮. እንደዚህ ሲያደርጉ ቢገኙ ይገ ሠጹ ዲያቆኑም ተነሥቶ ይጾሙ ዘንድ ይዘዛቸው::

፸፯. ካህናትም እንደዚሁ የሰው ገን ዘብ ከሚነጥቁ ከሚለዋውጡ ከሴሰ ኞች አራጣን ቢቀበሉ ይገሠጹ፤ ለፈጣሪ እግዚአብሔርም ቊርባን አድርገህ አታግባው::

፹. ባልቴቶች ያለቆቻቸውን ቃል ለመስማት የተዘጋጁ ሁነው ያዘ ዟቸውን ሁሉ ይሠሩ ዘንድ የኤጲስ ቆጶሱንም ቃል ይጠብቁ ዘንድ የእግ ዚአብሔርም አገልጋይ እንደ መሆኑ ያከብሩት ዘንድ አግባብ ነው::

፹፩. ከበደለኞች ከከሐዲዎች ምጽ ዋትን የሚቀበል ቢኖር በነሱ ስሕ ተት ይሰነካከላል ፤ በበደላቸውም ይሞታል፣ ስለነሱም ጸሎትን ቢጸ ልይ ክርስቶስን ያሳዝነዋል::

፹፪. ነገር ግን ወደ ንስሐ ይመ ልሳቸው::

፹፫. ወደ ንስሐ ያልተመለሱትን በደለኞችን፣ ሐሰተኞችን፣ ኃጢአተኞ ችን፣ አድናቸው [illegible] የክፉ ሥራቸው ተካፋይ ይሆናል::



## አንቀጽ ፲ወ፬

በእንተ ከመ ኢ.መፍትው ያጥምቃ አንስት::

፩. ናሁ ንነግረክሙ ከመ ዐቢይ ኵነኔ ውእቱ ለእለ ይገብሩ ዘንተ ምግባረ::

፪. ወከመዝ ንኤዝዝ እንከ ከመ ኢ.ትግበሩ ዘንተ ምግባረ እስመ ዕል ወተ ሕግ ውእቱ ዝ ግብር እስመ ርእሳ ለብእሲት ብእሲ ዘይሠየም ክህነተ::

፫. ኢ.መፍትውኬ ንዕልዎ ለፈጣሪ ወንኅድግ ርእሰ ወንትሉ አባለ እስመ ብእሲት አባሉ ለብእሲ ወይ እቲ ወጽአት እምኔሁ ወእምኔሃ ይት ወለዱ ውሉድ እስመ ይቤ ውእቱኬ እግዚእነ::

፬. በከመ አቅደምነ ነጊረ ኢ.ታብ ሕዎን ለአንስት ይገሥጻ ወይም ሀራ ወኢይግበራ ግብረ ክህነት ዘኢ. እዙዝ ውስተ ሕግ::

፭. ወዘሰ ይገብር ከመዝ ዐለዎ ለእ ግዚአብሔር ወይክውን ከመ እለ አልቦሙ አእምሮ ወይሠይሙ አን ስተ ከመ ይኩና ካህናተ ለግልፎ ሥዕለ አንስት፣ ለእለ ከመዝ አርኅ ቅዎን እምሕጉ ለኢየሱስ ክርስ ቶስ ::

፮. ወበእንተዝ ግሙራ ኢ.መፍትው ያጥምቃ አንስት ወኢ.መነሂ::

## አሥራ አራተኛ አንቀጽ

ሴቶች ያጠምቁ ዘንድ እንዳይገባ ይናገራል::

፩. ይህን ሥራ ለሚሠሩት ሰዎች ጽኑ ቅጣት እንደሆነ እነሆ እንነግ ራችኋለን::

፪. እንደዚህ ያለ ሥራም እን ዳትሠሩ እናዝዛለን፣ ይህ ሥራ ሕግ ማፍረስ ነው፣ የሴት አለቃዋ ክህነትን የሚሾም ወንድ ስለሆነ::

፫. ፈጣሪን እንክደው ዘንድ አገባብ አይደለም፣ አለቃዋ የሚሆን ወንድን ትተን ሴትን ልንከተል አገባብ አይ ደለም፣ ሴት ለወንድ አካሉ ናትና፣ እርሷም ከእርሱ ተገኝታለችና፣ ከእር ሷም ልጆች ይወለዳሉ፣ እርሱ ጌታ ችን ብሏልና::

፬. አስቀድመን እደተናገርን ሴቶችን ያስተምሩ ይገሥጹ ዘንድ አታሰና ብቷቸው፣ በሕግ ያልታዘዘ የክህ ነት ሥራንም አይሥሩ::

፭. እንደዚህ የሚያደርግ ግን እግዚ አብሔርን ካደው ፤ በሴቶች አም ሳል ለተሠራ ጣዖት አገልጋዮች ይሆኑ ዘንድ ሴቶችን እንደሚሾሙ አእምሮ እንደሌላቸው ሰዎች ይሆ ናል፣ እንደዚህ ያሉትን ከኢየሱስ ክርስቶስ ሕግ ለዩዋቸው::

፮. ስለዚህም ሴቶች ማንንም ያጠ ምቁ ዘንድ አይገባም::

፯. ሶበሰ ብውሕ ያጥምቃ አንስት እምተጠምቀ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ እምኀበ እሙ ወእምኢተጠምቀ በኀበ ዮሐንስ::

፰. ወለነኒ እምኢፈነወነ ናጥምቅ ውስተ ዓለም፣ አላ ዳዕሙ እምፈነዎን ለአንስት ያጥምቃ ምስሌነ::

፱. ወንሕነኒ ንኤዝዘክሙ ኢይግበር ወኢመኑሂ ከመዝ::

፲. ወእመሂ ጥቀ ጠባባት ወቦን ሃይማኖት ወየአምራ መጻሕፍተ ኢናበውሖን ያጥምቃ ወይስብካ ወንጌለ::

## አንቀጽ ፲ወ፭

በእንተ ከመ ኢመፍትው ይግበር ሕዝባዊ ግብረ ክህነት ንኤዝዘክሙ እንከ::

፩. ኢይግበር ሕዝባዊ ግብረ ክህነት ኢያዕርግ ዕጣነ ወኢያጥምቅ ወኢያንብር እደ ወኢይባርክ ወኢየሀብ ኀብስተ በረከት::

፪. እስመ አልቦ ዘይክል ነሢአ ጸጋ ለእመ ኢተውህቦ እምኀበ እግዚአብሔር ::

፫. ወባሕቱ መፍትው ጸጋ ወክብረ ይንሥኡ በኀበ ኤጲስ ቆጶስ::

፯. ሴቶች ያጠምቁ ዘንድ የሚገባ ከሆነስ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከእናቱ ዘንድ በተጠመቀ ነበር፣ ከዮሐንስም ዘንድ ባልተጠመቀ ነበር::

፰. እኛንም እናጠምቅ ዘንድ ወደ ዓለም ባልላከንም ነበር፣ ነገር ግን ከኛ ጋራ ያጠምቁ ዘንድ ሴቶችን በላካቸው ነበር እንጂ::

፱. እኛም ማንም እንደዚህ እንዳ ያደርግ እናዝዛችኋለን::

፲. ፈጽመው ብልሆችም ቢሆኑ ሃይማኖትም ቢኖራቸው፣ መጻሕፍትንም ቢያውቁ፣ ያጠምቁና ወንጌልን ያስተምሩ ዘንድ አናሰናብታቸውም ::

## አሥራ አምስተኛ አንቀጽ

ሕዝባዊ የክህነትን ሥራ ይሠራ ዘንድ እንዳይገባው ይናገራል::

፩. ሕዝባዊ የክህነት ሥራን እንዳይሠራ፣ ዕጣንንም እንዳያሳርግ ፣ እንዳያጠምቅ ፣ በአንብሮተ እድም እንዳይባርክ፣ በረከተ ኅብስቱንም እንዳይሰጥ እናዝዛችኋለን::

፪. ከእግዚአብሔር ዘንድ ካልተሰጠው የእግዚአብሔርን ጸጋ ገንዘብ ማድረግ የሚቻለው የለምና::

፫. ነገር ግን ጸጋንና ክብርን ከኤጲስ ቆጶሱ ዘንድ ይቀበሉ::



፬. ወዘሰ ኢተውህቦ ሢመተ ክህነት ለእመ ተዐደወ ይረክብ ኵነኔ ከመ ዖዝያን ንጉሥ::[፭]

፭. ወዓዲ ኢአዘዝነ ያጥምቁ ኵሎሙ ሠዩማነ ቤተ ክርስቲያን ወኢአናጉንስጢሳውያን ፣ ወኢመዘምራን ወኢዐጸውተ ኆዋኅው::

፮. አላ ያጥምቁ ኤጲስ ቆጶሳት ወቀሳውስት ባሕቲቶሙ፣ ወዲያቆናትኒ ይትለአኩ ምስሌሆሙ ኅቡረ::

፯. ወእለሰ ይትዐደዉ ወይገብሩ ከመዝ ይረክቡ ኵነኔ ዘረከቦሙ ለደቂቀ ቆሬ::

፰. ናሁ ንኤዝዝ ኢይሢሙ ቀሲሳን ዲያቆናተ ወዲያቆናዊተ ወኢአናጉንስጢሰ ወመዘምራነ ወኢዐጸውተ ኆዋኅው::

፱. አላ ኤጲስ ቆጶሳት ይሢሙ በሥርዐተ ቤተ ክርስቲያን እለ አልቦሙ ቂም ወቅንዓት ወኢሐሜት ወኢጽልዕ ኢእከይ::

፲. ናሁ አቅደምነ ነጊሮቶሙ እስመ እለ ይገብሩ ከመዝ ይከውኑ ነኪራነ እምሕዝበ ክርስቲያን ወፈድፋደሰ ለመበለታት::

፬. ያልተሰጠውን የክህነት ሹመትን ቢደፋፈር ግን እንደ ንጉሥ ዖዝያን ፍዳን ይቀበላል::

፭. ዳግመኛም የቤተ ክርስቲያን ሹማምንት ሁሉም ያጠምቁ ዘንድ አላዘዝንም፣ አናጉንስጢሶች መዘምራንም፣ በር ዘጊዎችም ቢሆኑ ::

፮. ኤጲስ ቆጶሳትና ቀሳውስት ብቻ ያጥምቁ እንጂ ዲያቆናት ግን ከነሱ ጋር በአንድነት ይላላኩ::

፯. ተደፋፍረው እንደዚህ የሚያደርጉ ግን የቆሬን ልጆች ያገኛቸውን ፍዳ ያገኛሉ::

፰. ቀሳውስት ዲያቆናትንና ዲያቆናዊትን፣ አንጉንስጢስንም፣ መዘምራንንም በር ዘጊዎችንም እንዳይሾሙ እነሆ እናዝዛለን::

፱. በቤተ ክርስቲያን ሥርዓት ቂምና ቅንዓት ፣ ሐሜትም ፣ ፀብና ክፋትም የሌላቸውን ኤጲስ ቆጶሳት ይሹሙ እንጂ ::

፲. እነሆ አስቀድመን ነግረናቸው እንደዚህ የሚያደርጉ ሰዎች ከክርስቲያን ወገኖች የተለዩ ይሆናሉና ይልቁንም ለባልቴቶች::

---

፭ ዜና መዋ. ካልዕ፡ ፳፮ ፥ ፳

## አንቀጽ ፲ወ፮
## በእንተ መዓስብ፤

፩. እስመ ሰይጣን የኀሥሥ ምክንያተ በዘያሠግር በከመ ገብረ ትካት ላዕለ ቃየል።

፪. እስመቦ እለ ይብላ መበለታት ንሕነ ወእማንቱሰ ይገብራ ግብረ ዘኢይደልዎን ለመበለታት በከመ ገብረ ቃየል ዘኢይደሉ በእኁሁ።

፫. እሎንኬ እለ አልቦን አእምሮ እስመ አኮ በተሰምዮ መበለታት ዘይበውኣ መንግሥተ ሰማይ አላ በርትዕት ሃይማኖት ወበሠናይ ምግባር።

፬. ወእንተሰ ነሥአት ስመ መበለት ወትገብር ምግባረ ሰይጣን ዛቲኬ ሐሳዊተ ስም ወትረክብ ኵነኔ ዘለዓለም።

፭. ናሁ ንሰምዕ ከመቦ እምውስተ መበለታት እኩያት ቀናዕያት ወመስተዋድያት እለ ይገብራ ጋዕዘ ማዕከለ አኃው እማንቱኬ ኢኮና እምክርስቶስ እስመ ኢዐቀባ ቃለ ተግሣጽ።

፮. ወእመቦ እምአኀት እለ ርእያ እንዘ ይትወሀባ ምጽዋት ለእኅቶን መበለታት፤ እመኒ ወርቅ አው አልባስ፤ አው መብልዕ ወመስቴ፤ ወእምዝ ተፈሥሐት ወረከበት ዕረፍተ መፍትው ከመዝ ይበላ፤ ይትባረክ እግዚአብሔር አምላክነ ዘጸገዋ ዕረፍተ ወትፍሥሕተ ለፍቅርት እኅትነ መበለት።

## አሥራ ስድስተኛ አንቀጽ፤
## የፈትን ነገር ይናገራል

፩. ሰይጣን ቀድሞ በቃየል ላይ እንዳደረገ ሰውን የሚያጠምድበትን ምክንያት ይፈልጋልና።

፪. እኛ መበለታት ነን የሚሉ አሉና ቃየል በወንድሙ የማይገባ እንዳደረገ እነሱ ግን ለመበለታት የማይገባውን ሥራ ይሠራሉ።

፫. ዕውቀት የሌላቸው እሊህ ናቸው፤ መበለታት በመባል መንግሥተ ሰማይ አይገቡምና፤ በቀናች ሃይማኖትና በበጎ ሥራ ነው እንጂ።

፬. የበመለትን ስም ይዛ የሰይጣንን ሥራ የምትሠራ ግን ይህቺ የስም ሐሰተኛ ናት የዘላለም ፍዳንም ትቀበላለች።

፭. እንሆ ከመበለቶች ወገን ክፉዎች ቀናተኞችና ነገረ ሠሪዎች በወንድማማቾች መካከል ክርክርን የሚያደርጉ እንዳሉ እንሰማለን፤ እሊህ ከክርስቶስ አይደሉም ፤ የተግሣጽ ቃልን አልጠበቁምና።

፮. ከእኅቶች ወገን እኅታቸው ለሆነች መበለት ምጽዋት ሲሰጣት ያዩ ቢኖሩ፤ ወርቅም ቢሆን፤ ልብስም ቢሆን፤ መብልም መጠጥም ቢሆን፤ ከዚህ በኋላ ደስ ቢላት ዕረፍትንም ብታገኝ፤ ለተወደደች ደሀ እህታችን ዕረፍትንና ደስታን የሰጣት ፈጣሪያችን እግዚአብሔር ይክበር ይመስገን ይሉ ዘንድ እንዲህ ይገባል።



፯. ኦ እግዚኦ ባርክ ወአክብር ላዕለ ዘወሀብካ ለዛቲ መበለት ወአብዝኅ ንዋየ በጽድቅ ወበንጽሕ ወተዘከራ በሠናያቲከ ወዕበየ ሣህልከ ወምሕረትከ ።

፰. ወለዝንቱኒ ኤጲስ ቆጶስ ሀቦ ምክዕቢተ ክብር ለዘመሀረ ወገሠጸ ወለዘጸገወነ ሀቦ አክሊለ ምክሕ አመ ይፈልስ እምዝንቱ ዓለም።

፱. ወከማሁ ዛቲኒ መበለት ትጸሊ ወታስተብቍዕ ምስሌሆሙ በእንተ እለ ይገብሩ ላዕሌሃ ምሕረተ ወይእቲኒ ተሀብ ለጽኑሳን እምዘ ነሥአት።

፲. ወበእንተዝ ይከውን ሥሙረ ምግባራ በቅድመ እግዚአብሔር እስመ ጽሑፍ ዘይብል ዘትገብር የማንከ ኢታእምር ፀጋምከ ወይኩን ክዱነ ምጽዋትከ።

፲፩. ከመዝ ትጸሊ መበለት ዲበ እለ ወሀብዋ ወመጽወትዋ እስመ አርአያ መቅደሱ ይእቲ በከመ ጽሑፍ ዘይብል አቡከ ዘይሬእየከ በኅቡእ የዐስየከ ክሡተ።[፩]

፲፪. መበለታትሰ እለ ኢየሐውራ በትእዛዘ እግዚአብሔር ይቀንዓ ላዕለ ዘመጽወተ ለእኅቶን የኀሥሣ ወይብላ መኑ ዘገብረ ምስሌሃ ዘንተ ምሕረተ።

፯. ጌታ ሆይ ለዚች ድኃ በሰጠሃት ላይ ባርክ አክብርም፤ ገንዘቡንም በእውነትና በንጽሕና አብዛው፤ በበጎነትህና በይቅርታህ ብዛት በቸርነትህም አስባት።

፰. ለአስተማረና ለመከረ፤ ለዚህም ኤጲስ ቆጶስ እጽፍ ድርብ ክብርን ስጠው፤ ለሰጠንም ሰው ከዚህ ዓለም በሞት ተለይቶ በሚሔድበት ጊዜ የመመኪያ አክሊልን ስጠው።

፱. ይህች መበለትም በእርሷ ላይ ቸርነትን ለሚያደርጉ ሰዎች ከእነርሱ ጋራ ትጸልይ፤ ትማልድ፤ እርሷም ከተቀበለችው ለተቸገሩት ትስጥ።

፲. ስለዚህም በእግዚብሔር ፊት ሥራዋ የተወደደ ይሆናል፤ ቀኝ እጅህ የምታደርገውን ግራ እጅህ አትወቅብህ ፤ ምጽዋትህም የተሰወረ ይሁን ተብሎ ተጽፎአልና።

፲፩. መበለት በሰጧትና በመጸወቷት ሰዎች ላይ እንደዚህ ትጸልይ፤ የቤተ መቅደሱ ምሳሌ ናትና፤ ተሰውረህ ስትመጸውት የሚያይህ አባትህ ዋጋህን ገልጦ ይሰጥሃል ተብሎ እንደ ተጻፈ።

፲፪. በእግዚአብሔር ትእዛዝ ጸንተው የማይኖሩት መበለታት ግን ለእኅቶቻቸው በመጸወተ ሰው ላይ ሥጋዊ ቅንዓትን ይቀናሉ፤ ለእርሷ ቸርነትን ያደረገ ማነው?እያሉ ይፈልጋሉ።

---

፩. [illegible]

፲፫. ወእምዝ ሶበ ለበዋ ወአእመራ ኀበ ዘመጽወተ ለእኀቶን የሐውራ ወያጽሕባሁ ወይብላሁ እፎ ቀደምከ ውሂበ ለዛቲ እንዘ ፈድፋደ ጽኑሳት ነሕነ እምኔሃ::

፲፬. እስመ አብዳት እማንቱ እለ ይብላ ከመዝ እንዘ ይመስሉን ሀብት ዘእምንበ ሰብእ አላ ሀብተ ጸጋስ እምኀበ እግዚአብሔር ውእቱ::

፲፭. ወእመሰ ነዳዪት ይእቲ ጥዩቀ ኢመፍትው ይሑራ ያጽሕባሁ ለዘገብረ ምሕረተ አላ ባሕቱ ርቱዕ ይንበራ ውስተ ቤቶን::

፲፮. ወይስግዳ በገጾን ወይነስሓ ወይስኣላሁ ለእግዚአብሔር እስመ ገብረ ምሕረተ እግዚአብሔር ከመ ይዜንዋ ሠናያቲሁ::

፲፯. ይቤ እግዚእነ ሶበ ትበውኡ ውስተ ቤት በሉ ሰላም ለዝንቱ ቤት::

፲፰. "ወእመቦ ህየ ውሉደ ሰላም ያዕርፍ ሰላምክሙ ላዕሌሁ::"

፲፱. ወእመ አኮሰ ይግባዕ ሰላም ኀቤክሙ፣ ወእመሰ ሰላም ኢረከበት ድልወ ኀበ ተዐርፍ ትገብእ ኀበ ዘፈነዋ፣ ከማሁ ውእቱ መርገም በዐመፃ ኢይበጽሕ ላዕለ ዘኢአበሰ አላ ዳዕሙ ይገብእ ኀበ ዘረገመ::

፲፫. ከዚህም በኋላ እኅታቸውን የመጽወተውን ሰው አስተውለው ባወቁ ጊዜ ሔደው "ከእርሷ ይልቅ ፈጽመን የተቸገርን እኛ ሳለን ለዚህች እንደምን አስቀድመህ ሰጠህ" እያሉ ያስቸግሩታል::

፲፬. ሀብት ከሰው ዘንድ የሚሰጥ መስሏቸው እንዲህ የሚሉ ሴቶች አላዋቂዎች ናቸው፣ የጸጋ ሀብት ግን ከእግዚአብሔር ዘንድ ነው::

፲፭. ይህች ፈጽማ የተቸገረች ብትሆን ግን ቸርነት ያደረገውን ሰው ለማስቸገር ይሄዱ ዘንድ አይገባም፣ በቤታቸው ውስጥ ይቀመጡ ዘንድ ይገባል እንጂ::

፲፮. በግንባራቸው ወድቀው ይስገዱ፣ ንስሓም ገብተው እግዚአብሔርን ይለምኑት፣ ቸርነቱን ይነግሩ ዘንድ እግዚአብሔር ምሕረትን አድርጓልና::

፲፯. ጌታችን ወደ ቤት በገባችሁ ጊዜ "ለዚህ ቤት ሰላም ይሁን" በሉ አለ::

፲፰. የሰላም ልጅ ቢኖርም ሰላማችሁ በላዩ ይደርበት::

፲፱. ይህ ባይሆን ግን ሰላማችሁ ወደ እናንተ ይመለስ፣ ሰላም ታድርበት ዘንድ የተዘጋጀ ባታገኝ ግን ወደላካት ትመለሳለች፣ እንደዚሁም የዐመፅ ርግማን ባልበደለ ሰው ላይ አይደርስም፣ ወደ ረጋሚው ይመለሳል እንጂ ::



፳. ዘይረግም ባዕደ ከንቶ ረገመ ርእሶ በከመ ይቤ ሰሎሞን ከማሁ አንትሙኒ በከመ ገበርክሙ ለካልኣን ከማሁ ትትፈደዩ::

፳፩. እስመ ይቤ ግበ ከረየ ወደሀየ ወይወድቅ ውስተ ግብ ዘገብረ ወይገብእ ፃማሁ ዲበ ርእሱ ወትወርድ ዓመፃሁ ዲበ ድማሁ::

፳፪. እስመ ዘይከሪ ግበ ለቢጹ ይወድቅ ውስቴቱ ወዘይፈርህ መርገመ ኢይርግም ባዕደ::

፳፫. ወዘይጸልእ ለርእሱ ኢይግበር ዲበ ባዕድ::

፳፬. ወበእንተዝ አንተኒ ኤጲስ ቆጶስ መምህር ገሥፆን ለእለ ይሜንንዎን ለመበለታት ::

፳፭. ወተዐገሥሙ ለምጽኣን ወሐውጾሙ ለሕሙማን ወተፈሣሕ በኀሩያን እለ ይባርኩ ወኢይረግሙ ወአዝዞሙ ከመ ኢይግበሩ እኩየ ላዕለ ሰብእ ዳዕሙ ይግበሩ ሰላመ::

፳፮. ወእመሂ ኤጲስ ቆጶስ አው ቀሲስ፣ ወእመሂ ዲያቆን አው ዘኮነ እምሥዩማን፣ ኢይፃእ እም አፉሁ መርገም ከመ ኢይረስ መርገመ ህየንተ በረከት ::

፳. በከንቱ ሌላውን የሚረግም ሰው ራሱን ረገመ፣ ሰሎሞን እናንተ በሌላው እንደሠራችሁ እንደዚሁ ፍዳችሁን ትቀበላላችሁ እንዳለ::

፳፩. "ጉድጓድን ቈፈረ አጐደጐደም፣ በቈፈረው ጉድጓድ ውስጥም ይወድቃል፣ ድካሙም በራሱ ላይ ይመለሳል፣ በደሉም በአናቱ ላይ ይወርዳል ብሏልና::"

፳፪. ለባልንጀራው ጉድጓድን የሚምስ ሰው እርሱ በውስጡ ይወድቃልና መርገምንም የሚፈራ ሌላውን አይርገም::

፳፫. ለራሱ የሚጠላውን በሌላው አያድርግ ::

፳፬. ስለዚህም መምህር የምትሆን አንተ ኤጲስ ቆጶስ ሆይ፣ መበለታትን የሚንቁትን ምከራቸው::

፳፭. ወደ ቤተ ክርስቲያን የመጡትን ታገሣቸው ፣ የታመሙትንም ጐብኛቸው፣ በማይረግሙ በሚመርቁ በተመረጡ ሰዎች ደስ ይበልህ፣ በሰዎች ላይም ክፉ ሥራን እንዳይሠሩ እዘዛቸው፣ ሰላምን ያድርጉ እንጂ ::

፳፮. ኤጲስ ቆጶስም ቢሆን፣ ወይም ቄስ፣ ወይም ዲያቆን ቢሆን፣ ከሹማምንት ወገንም የሆነ ቢሆን፣ ስለበረከት ፈንታ እርግማንን እንዳይወርስ እርግማን ከአፉ አይውጣ::

፳፯. መፍትው ለኤጲስ ቆጶስ ይገሥጾሙ ወይምህሮሙ ወይናዝዞሙ ለሕዝብ ኢይፃዕ እምአፉሁ ቃለ መርገም ::

፳፰. አላ ይተክዝ በእንተ ካህናት ወዲያቆናት ወደናግል ወመበለታት ወሕዝብ::

፳፱. ወበእንተዝ ኤጲስ ቆጶስ አመክሮሙ ለዲያቆናት እለ ይትቀነዩ ምስሌከ ወርድኦሙ በገቢረ ሠናይ ከመ ድልዋነ ይኩኑ ለተልእኮ ሕዝብ::

፴. ወዓዲ ዲያቆናዊትኒ ትሠየም ወይእቲ ኅሪት ወንጽሕት እንተ አልባቲ ነውር ለተልእኮ አንስት::

፴፩. እስመ ኢመፍትው ዲያቆን ይትለአክ ለአንስት ከመ ኢይኩን ሐሜት ለእለ ኢየአምኑ::

፴፪. በእንተዝኬ ትኩን ዲያቆናዊት ልእክተ ለአንስት ወትቅብዖን ቅብዐ ወታልብሶን አልባሲሆን እምድኅረ ጥምቀት::

፴፫. ወአንተሰ ኤጲስ ቆጶስ ቅባዕ ፍጽሞን ለእለ ይጠመቃ አንስት በቅብዕ ቅዱስ በከመ ሥርዓተ ቅድስት ጥምቀት::

፴፬. ወእምድኅረዝ አንትሙኒ ኤጲስ ቆጶሳት ወቀሲሳን ጸልዩ ላዕለ እምታሕቴክሙ ወአጥምቅዎሙ በስመ አብ ወወልድ መንፈስ ቅዱስ::

፳፯. ለኤጲስ ቆጶስ የዕርግማን ቃል ከአፉ ሳይወጣ ሕዝቡን ይመክራቸው ፣ ያስተምራቸው ፣ ያጽናናቸውም ዘንድ ይገባል::

፳፰. ነገር ግን ስለ ካህናት፣ ስለ ዲያቆናት፣ ስለ ደናግል፣ ስለ ባልቴቶችና ስለ ሕዝቡም ይዘን እንጂ::

፳፱. ስለዚህም ኤጲስ ቆጶስ ሆይ ሕዝቡን ለማገልገል የተዘጋጁ ይሆኑ ዘንድ ካንተ ጋራ የሚገዙ ዲያቆናትን ምከራቸው፤ በበጎ ሥራም አገዛቸው::

፴. ዳግመኛም ዲያቆናዊት ትሾም፣ ይህችም ነውር የሌለባት ሴቶችን ለማገልገል የተመረጠች ንጽሕት ትሁን::

፴፩. ዲያቆን ለማያምኑ ሰዎች ሐሜት እንዳይሆን ለሴቶች መላክተኛ ይሆን ዘንድ አይገባምና::

፴፪. ስለዚህ ነገር ዲያቆናዊት ለሴቶች መላክተኛን ትሁን፣ ዘይቱን ትቀባቸው፣ ከተጠመቁም በኋላ ልብሳቸውን ታልብሳቸው::

፴፫. አንተ ግን ኤጲስ ቆጶስ የሚጠመቁትን ሴቶች እንደ ቅድስት ጥምቀት ሥርዐት ቅብዕ ቅዱስን ቅባቸው::

፴፬. ከዚህም በኋላ እናንተ ኤጲስ ቆጶሳት ቀሳውስት በበታቾቻችሁ ላሉት ጸልዩላቸው፤ በአብ በወልድ በመንፈስ ቅዱስ ስምም አጥምቋቸው::



፴፭. ወእምዝ ይትመጠዎሙ ዲያቆን ለዕደው፣ ወዲያቆናዊትኒ ትትመጠዎን ለአንስት ከመ ይኩን ማኅተም ዘነሥኡ ቅዱሰ ወንጹሐ ዘኢይክል ይግሥሦ ወኢመኑሂ::

፴፮. ወእምድኅረ ተጠምቀ ይቅብዖሙ ኤጲስ ቆጶስ በቅብዐ በለሳን እስመ ተጠምቀ ለክርስቶስ በሞቱ::

፴፯. ወዝንቱ ቅብዕ ዘእምቅብዐ በለሳን ኃይለ ሃይማኖት ውእቱ፣ እስመ ሶበ ንወጽእ እማይ አምሳሊሁ ለክርስቶስ ውእቱ ዘአንሥኦ አብ እሙታን ዘላዕለ ኵሉ::

፴፰. ዝውእቱ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወልድ ዋሕድ እግዚአ ሕይወት::

፴፱. ወጰራቅሊጦስ መንፈሰ ጽድቅ ዘተፈነወ እምኀበ አብ ይምህር ኵሎ ::

፵. ወእለሰ ተጠምቁ ይርኃቁ እምዕልወት ወይንጽሑ እምኃጢአት ወይኩኑ አዕርክቲሁ ለእግዚአብሔር ወጸላእያኒሁ ለዲያብሎስ ወመዋርስቲሁ ለክርስቶስ ዐላውያኒሁ ወከሐድያኒሁ ለሰይጣን ወመቀጥቅጣነ መናግንቲሁ ወእሙንቱ ይከውኑ ንጹሓነ ዘእንበለ ርኵስ ወይሰመዩ ውሉደ [illegible]

፴፭. ከዚህም በኋላ ዲያቆኑ ወንዶችን ይቀበላቸው፣ ዲያቆናዊትም ሴቶችን ትቀበላቸው፣ የተቀበሉት ማኅተም (ሜሮን) ማንም ማን ሊዳስሰው የማይችል ንጹሕ ቅዱስ ይሆን ዘንድ::

፴፮. ከተጠመቁም በኋላ ኤጲስ ቆጶሱ ቅብዐ ሜሮኑን ይቀባቸው፣ በክርስቶስ በሞቱ አምሳል ተጠምቀዋልና::

፴፯. ይኸውም ከበለሳን የተገኘ ቅብዓ ሜሮን የሃይማኖት ኃይል ነው፣ ተጠምቀን ከውኃ በወጣን ጊዜ ከሁሉ በላይ የሚሆን አብ ከሙታን ለይቶ ያስነሣው የክርስቶስ ምሳሌ ነውና::

፴፰. ይኸውም የሕይወት ጌታ አንድ ልጅ ኢየሱስ ክርስቶስ ነው::

፴፱. የእውነት መንፈስ ጰራቅሊጦስም ሁሉን ያስተምር ዘንድ ከአብ ዘንድ የሚላክ ነው::

፵. የተጠመቁቱ ግን ከክህደት ይራቁ ከኀጢአትም ይንጹ፣ የእግዚአብሔር ወዳጆችም ይሁኑ፣ የዲያብሎስም ጠላቶችና ሰይጣንን የሚክዱ፣ አሽከላውን የሚሰባብሩ የክርስቶስ ወራሾች ይሁኑ ፣ እነዚህ ያለ ኃጢአት ንጹሐን ይሆናሉ፤ የክርስቶስ ልጆችም ይባላሉ::

፺፩. ወዓዲ ይስአሉ ወያስተብቍዑ ኀበ አብ ከመ ይኩኑ አሐደ ኀብረተ ምስለ መሃይምናን ወይበሉ ከመዝ::

፺፪. አቡነ ዘበሰማያት ይትቀደስ ስምከ፣ ትምጻእ መንግሥትከ ወይኩን ፈቃድከ በከመ በሰማይ ከማሁ በምድር::

፺፫. ሲሳየነ ዘለለዕለትነ ሀበነ ዮም ኅድግ ለነ አበሳነ ወጌጋየነ ከመ ንሕነኒ ንኀድግ ለዘአበሰ ለነ ::

፺፬. ኢታብአነ እግዚኦ ውስተ መንሱት አላ አድኅነነ ወባልሐነ እምኵሉ እኩይ እስመ ዚአከ ይእቲ መንግሥት ኀይል ወስብሐት ለዓለመ ዓለም::[፫]

፺፭. መፍትውኬ ይኩኑ ዲያቆናት ንጹሓነ ወኄራነ ዘእንበለ ነውር ከመ ኤጲስ ቆጶስ::

፺፮. ወይትቀነዩ ወትረ ውስተ ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ወይፀመድዎ ለእግዚአብሔር በሠናይ መልእክት ወይፈጽሙ ግብሮሙ በጥበብ በ፩ ሕሊና ወበ፩ መንፈስ ወይለብዉ ዐስበ ቅኔሆሙ::

፺፯. ወኢይትዐበዩ ለተልእኮ ጽኑሳን በከመ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ኢመጽአ ከመ ይትለአክዎ ዳዕሙ ከመ ይትለአክ ወይመጡ ነፍሶ ቤዛ ብዙኃን ወዓዲ ኢአበየ ከመ ይመጡ ነፍሶ ህየንተ ዐርኩ ::[፬]

፺፩. ዳግመኛም ከምዕመናን ጋራ አንድነት ይሆኑ ዘንድ አብን ይለምኑ ይማልዱ፣ እንደዚህም ይበሉ::

፺፪. የሰማይ አባታችን ስምህ ይመስገን መንግሥትህ ትምጣ ፈቃድህም በሰማይ እንደሆነ እንዲሁ በምድር ይሁን::

፺፫. የዕለት ምግባችንን ዛሬ ስጠን፤ ኃጢአታችንንና በደላችንን ይቅር በለን፣ እኛም ለበደለን ይቅር እንል ዘንድ::

፺፬. አቤቱ ወደ ፈተና አታግባን፣ ከክፉ ሥራ ሁሉ ፈጽመህ አድነን እንጂ መንግሥት ኃይልና ጌትነት የአንተ ናትና ለዘለዓለም::

፺፭. ዲያቆናት እንደ ኤጲስ ቆጶሱ ያለነውር ንጹሓንና ቸሮች ይሆኑ ዘንድ አገባብ ነው::

፺፮. በቅድስት ቤተ ክርስቲያንም ዘወትር ያገልግሉ፣ በበጎ ተልዕኮም እግዚአብሔርን ያገልግሉት፣ በአንድ ሐሳብና በአንድ ልብ ሁነው በጥበብ ሥራቸውን ይፈጽሙ፣ የአገልግሎታቸውን ዋጋ ያስተውሉ::

፺፯. ለተቸገሩት ሰዎች ማገልገልንም እንቢ አይበሉ፣ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ሊያገለግል ስለ ብዙ ሰዎች ቤዛም ሰውነቱን ለሞት አሳልፎ ሊሰጥ ነው እንጂ ሊያገለግሉት እንዳልመጣ፣ ዳግመኛም ስለ ወዳጁ ነፍሱን አሳልፎ ይሰጥ ዘንድ እንቢ እንዳላለ የተቸገሩትን ለመርዳት እንቢ አይበሉ ::

፫. ማቴ. ፮፡፱–፲፫

፬. ማቴ. ፳፡፳፰



፺፰. እስመ እግዚአብሔር ወእግዚአ ሰማያት ወምድር ተዓገሠ ዘንተ ኵሎ በእንቲአነ እፎኬ አንትሙ ትትዔበዩ ለተልእኮ ነዳያን ወምስኪናን::

፺፱. መፍትው እንከ ትትመሰልዎ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ በኵሉ ግብር ዘተዓገሠ ከዊነ ገብር ወተወክፈ ንዴተ ወተፅናሰ ወተትሕተ ወፆረ ሕማማተ በዲበ ዕፀ መስቀል በእንቲአነ ከማሁ አንትሙኒ መፍትው ትትቀነዩ ለነዳያን አኃዊክሙ ወትትመሰልዎ ለክርስቶስ::

፻. ወዘሰ ይፈቅድ እምኔክሙ ይኩን ሊቀ ይኩንክሙ ገብረ::[፭]

፻፩. ወከማሁ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ፈጸመ ኵሎ ዘጽሑፍ በቃል ወበምግባር ወኮነ ገብረ ለብዙኃን ነሥአ ለንጸ ወቀነተ ወወደየ ማየ ውስተ ምሕፃብ ወቀደመ ሐፂበ እግረ አርዳኢሁ ወመዝመዘ በለንጽ ዘቀነተ ውስተ ሐቌሁ ከመዝ ገብረ ከመ ንትፋቀር በበይናቲነ ወመሀረነ ናፍቅር ቢጸነ::[፮]

፻፪. ወእመሰ እግዚእነ ወመድኅኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ ተትሕተ ወገብረ ዘንተ እፎኬ አንትሙ ትትዔበዩ ወትትሀከዩ ለገቢረ ሠናይ ለፅኑሳን ወለምንዱባን::

፺፰. የሰማያትና የምድር ጌታ ኢየሱስ ክርስቶስ ይህን ሁሉ ስለኛ ከታገሠ እናንተ ለድሆችና ለችግረኞች ማገልገል እንዴት እንቢ ትላላችሁ?

፺፱. ስለ እኛ አገልጋይ መሆንን ድህነትንና ችግርን የታገሠ፣ ራሱን ዝቅ ያደረገ፣ በመስቀል ላይ መከራዎችን የተቀበለ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስን በሥራውም ሁሉ ትመስሉት ዘንድ ይገባል፣ እንዲሁ እናንተም ድሆች ወንድሞቻችሁን ልታገለግሉ ክርስቶስንም ልትመስሉት ይገባል::

፻. ከናንተ ወገን አለቃን ይሆን ዘንድ የሚወድ ቢኖር አገልጋይ ይሁናችሁ::

፻፩. እንደዚሁም ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ የተጻፈውን ሁሉ በቃልና በሥራ ፈጸመ፤ ለብዙዎችም አገልጋይን ሆነ፣ መንዲሉንም አንሥቶ ታጠቀ፣ ውሀውንም በመታጠቢያው ጨመረ፣ የደቀ መዛሙርቱንም እግር ማጠብ ጀመረ፣ በወገቡ በታጠቀው መሐረሚያም አሸ፣ እንደዚህም ያደረገው እኛ እርስ በእርሳችን እንፋቀር ዘንድ ነው፣ ባልንጀራችንንም እንወድ ዘንድ አስተማረን::

፻፪. ጌታችንና መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ራሱን ዝቅ አድርጎ ይህን ካደረገ እናንተ ለተቸገሩና ለተጨነቁ ሰዎች በጎ ሥራን ለመሥራት እንዴት እንቢ ትላላችሁ? (ትታበያላችሁ) ?

፭. ማቴ. ፳፡፳፯

፶፫. ተቀነዩ እንከ በፍጹም ፍቅር ዘእንበለ ነጐርጓር ወነሢአ ገጽ::

፶፬. ወባሕቱ ኢትግበሩ ዘንተ ለነሢአ አርአያ ገጽ ዳዕሙ በእንተ እግዚአብሔር ከመ ትንሥኡ አስበ ፃማክሙ በኀቤሁ በደኃሪ ዕለት::

፶፭. መፍትው ይኅሥሡ ዲያቆናት ይግበሩ ፈቃዶሙ ዘእንበለ ይስአልዎሙ ነዳያን::

፶፮. ወዓዲ ይትቀነዩ ለኤጲስ ቆጶስ ወይኩኑ ፩ ነፍስ ወይረስይዎ አበ ወመምህረ ወመገሥጸ::

፶፯. ናሁ ንኤዝዝ ይሠየም ኤጲስ ቆጶስ በኀበ ፫ቱ ኤጲስ ቆጶሳት ወእመ አኮ በኀበ ፪ቱ::

፶፰. ወበኀበ ፩ዱ ኤጲስ ቆጶስሰ ኢይትከሀል ውሂበ ሢመት፣ እስመ በስምዐ ፪ወ፫ ይቀውም ኵሉ ነገር::[፯]

፶፱. ቀሲሳንሰ ወዲያቆናት ወባዕዳን ሥዩማነ ቤተ ክርስቲያን ይሠየሙ በኀበ ፩ዱ ኤጲስ ቆጶስ::

፷. ለቀሲሳንሰ ወለዲያቆናት ኢተውህበ ሎሙ ይሢሙ ሕዝባዌ አላ ባሕቱ ቀሲስ ይምሀር ወይገሥጽ ወይባርክ ሕዝበ ወይዕጥን ወያዕርግ መሥዋዕተ::

፶፫. እንግዲህ ያለማንጐራጐር ፊት አይቶ ያለማድላት በፍጹም ፍቅር ሁናችሁ አገልግሉ::

፶፬. ነገር ግን የፊት መልክን አይታችሁ ለማድላት አትሥሩ፣ በኋለኛይቱ ቀን የድካማችሁን ዋጋ ከእርሱ ትቀበሉ ዘንድ ስለ እግዚአብሔር ብላችሁ ነው እንጂ::

፶፭. ዲያቆናት ድኆች ሳይለምኗቸው ፈቃዳቸውን ሊያደርጉላቸው አገባብ ነው::

፶፮. ዳግመኛም ኤጲስ ቆጶሱን ያገልግሉ፣ አንድ ልብም ይሁኑ፣ አስተማሪና መካሪ አባትም ያድርጉት::

፶፯. እነሆ ኤጲስ ቆጶስ በሦስት ኤጲስ ቆጶሳት፣ ያም ባይሆን በሁለት ኤጲስ ቆጶሳት ይሾም ዘንድ እናዝዛለን::

፶፰. በአንድ ኤጶስ ቆጶስ ግን የኤጲስ ቆጶስነት ሹመት መስጠት አይቻልም፣ ነገር ሁሉ በሁለት ወይም በሦስት ምስክር ይጸናልና::

፶፱. ቀሳውስት፣ ዲያቆናትና ሌሎች የቤተ ክርስቲያን ሹማምት ግን በአንድ ኤጲስ ቆጶስ ይሾሙ::

፷. ለቀሳውስትና ለዲያቆናት ግን ሕዝባዊውን ይሾሙ ዘንድ ሥልጣን አልተፈቀደላቸውም ነገር ግን ቄስ ያስተምርና ይመክር፣ ሕዝቡን ይባርክና ያጥን፣ መሥዋዕቱን ያሳርግ ዘንድ ነው እንጂ::

---

፯ ማቴ. ፲፰፥፲፯



፷፩. ወዲያቆንሰ አልቦ ዘይገብር ወኢምንትኒ ዘእንበለ ተልእኮ ለኤጲስ ቆጶስ ወለቀሲሳን ወይፈጽም በሠናይ መልእክቶ::

## አንቀጽ ፲ ወ፯
### በእንተ ዕጓለ ማውታ

፩. መፍትው ሕዝበ ክርስቲያን እለ አልቦሙ ውሉድ ይሕፅንዎሙ ለዕጓለ ማውታ ወለወራዙት ወለደናግል ወይረስይዎሙ ከመ ደቂቆሙ ወፈድፋደ ያፍቅርዎሙ::

፪. ወዘቦሰ ውሉድ ወበጽሐ አምጣነ ውርዙት ያውስብ ድንግለ ዕጓለ ማውታ::

፫. ወእመሰ ገበርክሙ ከመዝ ፈጸምክሙ ዐቢየ ግብረ ወትከውኑ አበ ለዕጓለ ማውታ ወትረክቡ ዐስበ ህየንተ ዘተቀነይክሙ በኀበ እግዚአብሔር አምላክ::

፬. ወእመሰቦ ዘይትሜካሕ ወይሜንን ዕጓለ ማውታ፣ ወይብል አንሰ ኢያወስብ ነዳዪተ፣ ይለቡ እንከ መኑ ውእቱ አብ ለዕጓለ ማውታ፣ ወቀዋሚሃ ለመዓስብት፣ እስመ ዘይኄሊ ይግበር ከመዝ ይዘሩ ብዕሎ ለባዕድ ወይትፌጸም ላዕሌሁ ዘይቤ መጽሐፍ፣ ለዘኢ.ብልዕዎ ቅዱሳን በልዕዎ [illegible]

፷፩. ዲያቆን ግን ለኤጲስ ቆጶሱና ለቀሳውስቱ ከመላላክ በቀር ምንም የሚያደርገው የለም ፣ መላላኩንም በመልካም ይፈጽም እንጂ::

## አሥራ ሰባተኛ አንቀጽ
### አባትና እናታቸው ስለሞቱባቸው ይናገራል፣

፩. ልጆች የሌሏቸው የክርስቲያን ወገኖች እናት አባት የሞቱባቸውን ልጆች ያሳድጓቸው ዘንድ ጐልማሶችንና ደናግልንም እንደ ልጆቻቸው አድርገው ፈጽመው ይወዷቸው ዘንድ አገባብ ነው::

፪. ወንድ ልጅ ያለው ቢኖር አካለ መጠን ቢያደርስም እናት አባቷ የሞቱባትን ድንግል ያግባ::

፫. እንደዚህ ብታደርጉ ግን ታላቅ ሥራን ፈጸማችሁ፣ እናት አባት ለሌለው ልጅም አባትን ትሆናላችሁ፣ በጎ አገልግሎትንም ስለ አገለገላችሁ በፈጣሪ እግዚአብሔር ዘንድ ዋጋችሁን ታገኛላችሁ::

፬. የሚመካ አባትና እናት የሌላትንም የሚንቅ፣ እኔስ ድኃዪቱን አላገባም የሚልም ቢኖር፣ እናትና አባት ለሞቱባትና ባሏ ሞቶባት ፊት ለሆነችው አባትና ጠበቃ ማን እንደሆነ ያስተውል፣ እንደዚህ የሚያስብ ሰው ገንዘቡን ለባዕድ ይበትናልና፣ ቅዱሳን ያልበሉትን የሶርያ ሰዎች ይበሉታል ብሎ መጽሐፍ የተናገረውም በእርሱ ላይ ይፈጸማል::

፳. እስመ ይቤ ኢሳይያስ ወለበሐውርቲክሙ ይበልዖ ፀር ነኪር በቅድሜክሙ።[፩]

### አንቀጽ ፲ ወ ፰

በእንተ ከመ መፍትው ይተክዙ ኤጲስ ቆጶሳት በእንተ ዕቤራት ወዕጓለ ማውታ።

፩. አንትሙኒ ኤጲስ ቆጶሳት ሐልዩ ሲሳዮሙ ለፅኑሳን ወግበሩ ትካዞሙ ወለዕጓለ ማውታ ሀቡ ርስተ ወንዋየ አበዊሆሙ ወለዕቤራትኒ ንዋየ አምታቲሆን።

፪. ወለወራዙት ወለደናግል ሥርዑ ሰብሳበ በከመ ይደሉ።

፫. ወለእለ ይትቀነዩ ሀቡ ዐስቦሙ ወአኅድርዎሙ ለነዳያን ወአብልዕዎሙ ለርኁባን ወአስተይዎሙ ለጽሙዓን ወአልብስዎሙ ለዕሩቃን ወሐውጽዎሙ ለሕሙማን ወርድእዎሙ ለሙቁሓን።

፬. ዘንተ ሐልዩ ወከመዝ ግበሩ ለዕጓለ ማውታ ወለዕቤራት መዓልተ ወሌሊተ እስመ ዘይክል ገቢረ ከመዝ ብፁዕ ውእቱ።

፭. ወብፁዕ ናሁኬ አድኅነ ርእሶ እስመ ተወክፈ ዕቤረ ወዕጓለ ማውታ ወነግደ።

፳. ኢሳይያስ ልዩ ጠላት አገሮቻቸሁን በፊታችሁ ይበላዋል ብሎ አልና ።

### አሥራ ስምንተኛ አንቀጽ

ኤጲስ ቆጶሳት አባት እናት ስለሞቱባቸው ልጆችና ባልቴቶች ይተክዙ ዘንድ አገባብ እንደሆነ ይናገራል።

፩. እናንተ ኤጲስ ቆጶሳት ለተቸገሩት ሰዎች ምግባቸውን አስቡ፣ ግዳጃቸውንም አድርጉ፣ ለድሃ አደጎችም የወላጆቻቸውን ገንዘብና ርስት ስጡ፣ ለባልቴቶችም የባሎቻቸውን ገንዘብ ስጡ።

፪. ለጎልማሶችና ለደናግልም እንደሚገባ ጋብቻን በሥርዐት አድርጉ።

፫. ለሚያገለግሉም ደመወዛቸውን ስጡ፣ ድሆችን አሳድሯቸው፣ የተራቡትንም አብሏቸው፣ የተጠሙትንም አጠጧቸው፣ የታረዙትን አልብሷቸው፣ የታመሙትን ጠይቋቸው፣ የታሠሩትንም ርዷቸው።

፬. ይኸን አስቡ፣ ለድሃ አደጎችና ለባልቴቶችም በሌሊትና በቀን እንደዚህ ማድረግ የሚችል ሰው ብፁዕ ነውና።

፭. እነሆ ብፁዕ የተባለ ሰውም እራሱን አዳነ፣ ባልቴቷንና ድሃ አደጉን እንግዳውንም ተቀብሏልና።

፩. ኢሳ. ፩፥፯



፮. ወበእንተዝ ይቤ እግዚእነ ውሂብስ እምረኪብ ውእቱ።[፩]

፯. ወእለሰ ይትዔገሉ ነዳያነ ይትኴነኑ በቅድመ እግዚአብሔር በደኃሪት ዕለት።

፰. ወዘሰ ይጼኑ ወይነሥእ ምጽዋተ በከዊኖቱ ለዕጓለ ማውታ ወአረጋዌ ወድውየ ወለእመኒ ነዳይ ዘቦ ደቂቅ ለዘከመዝ ይገብር ኢትሕምይዎ እላ ነዐድዎ እስመ ኮነ ምሥዋዐ ለእግዚአብሔር።

፱. ውእቱ ርቱዕ ይጸሊ ኵሎ ጊዜ ዘእንበለ ሐኬት በእንተ እለ ወሀብዎ ምጽዋተ።

፲. ወዘሰ እንዘቦ ይነሥእ ምጽዋተ ሎቱኒ ይትሐሰቦ እግዚአብሔር እስመ መሰጠ ኅብስተ ነዳይ ወኢገብረ ሠናየ ለርእሱ ወኢለባዕዳን።

፲፩. ወዘሂ ቦ ንዋይ ወኢይጼጉ ለጽኑሳን ይመስል ከመ ባዕል ዘአስተጋብአ ወመልዐ መዛግብቲሁ በከንቱ ወይከውን ሙሱነ በኀበ እግዚአብሔር እስመ ኢይበቍዖ ንዋዩ በዕለተ መዓቱ ለእግዚአብሔር።

፲፪. ወዘሰ ይገብር ከመዝ ኢየአምን በእግዚአብሔር አላ ዳዕሙ ውእቱ ያመልክ ንዋዮ ወይትዌከል ቦቱ።

፮. ስለዚህም ጌታችን እንዲህ አለ፣ መስጠት ከማግኘት የተነሣ ነው።

፯. ድሆችን የሚቀሙ ግን በኋለኛዋ ቀን በእግዚአብሔር ፊት ይፈረድባቸዋል።

፰. ድሃ አደግና ሽማግሌ በሽተኛም በመሆኑ ወይም ልጆች ያሉት ድሃ በመሆኑ ምጽዋት ቢቀበል እንደዚህ የሚያደርገውን አትሙት፣ ነገር ግን አድንቁት፣ ለእግዚአብሔር መሠውያ ሆኖአልና።

፱. እርሱም ምጽዋትን ስለሰጡት ያለ ቸልታ ሁልጊዜ ይጸልይ ዘንድ ይገባል።

፲. ነገር ግን እያለው ምጽዋትን የሚቀበል እርሱን እግዚአብሔር ይቆጣጠረዋል፣ የድሃውን ምግብ ነጥቋልና፣ ለራሱና ለሌሎችም በጎ ነገርን ስላላደረገ።

፲፩. ገንዘብ ያለው ለተቸገሩትም የማይሰጥ ሰብስቦ ሣጥኖቹን በከንቱ እንደሞላ በእግዚአብሔርም ዘንድ እንደሚጠፋ ባለጸጋን ይመስላል፣ ገንዘቡ እግዚአብሔር በተቆጣበት ቀን አይጠቅመውምና።

፲፪. እንደዚህ የሚያደርግም በእግዚአብሔር አያምንም ነገር ግን ገንዘቡን ያመልካል፣ በገንዘቡም ይታመናል።

፩ ፪ቆሮ. ፰፥፲፩ ፤ ግብ. ሐዋ. ፳፥፴፭

፲፫. ኢያፈቅር ርትዐ ወይነሥእ ገጸ ወአልቦ ምሕረት ወኢይሬኢ ፍርሀተ እግዚአብሔር ቅድመ አዕይንቲሁ ወአልቦ ፍቅረ ጸላኢ ለርእሱ ወአልቦ ዐርክ::

፲፬. ወዘሰ ይገብር ከመዝ ይማስን ንዋዩ ወይበልያ ፀር ነኪር እመኒ እንዘ ሕያው ውእቱ አው እም ድኅረ ሞተ እስመ ይቤ ዘያስተጋብእ ብዕሎ በዐመፃ ይትሐየድ ብዕሉ እምኔሁ::[፪]

## አንቀጽ ፲ ወ ፱

በእንተ ከመ መፍትው መዓስብ ወመበለታት ይንሥኡ ዘተጸገዋ በአኰቴት::

፩. ንገሥጸን ለመበለታት ወለመ ዓስብ ይትወከፉ ዘወሀቦን እግዚአ ብሔር በአኰቴት በፍርሀት ወበረ ዓድ ወያአኵታሁ ለእግዚእ ዘይሁብ ሲሳየ ለርኁባን::

፪. መኑ እምኔክሙ ዘይበልዕ ወይ ሰቲ በአቅም አኮኑ ውእቱ ዘጸገዎ እግዚአብሔር ዘይሰፍሕ እደዊሁ ወያ በዝኅ ሠናያተ በፈቃዱ ዘይሁብ ሥር ናየ ለወራዙት በፈቃዱ ወወይነ ለደና ግል ወቅብዐ ትፍሥሕት ለሕያዋን ጽጋበ ለእንስሳ ወግዕዛነ ለአግብርት ወሥጋ ለአራዊት ወፍሬያተ ለአዕ ዋፍ ወሲሳየ ለኵሉ በከመ ይደሉ::

፪. ኢዮብ ፳፥፲፰

፲፫. ቅንነትን አይወድም፤ ነገር ግን ፊት አይቶም ያደላል፤ ምሕረትም የለውም፤ እግዚአብሔርን መፍራ ትንም በዓይኖቹ አያይም፤ ጠላትን ማፍቀርም ለራሱ የለውም ወዳ ጅም የለውም::

፲፬. እንደዚህ የሚያደርግ ሰው ገን ዘቡ ይጠፋል፤ በሕይወቱ ሳለም ቢሆን ወይም ከሞተ በኋላ ልዩ ጠላት ይበላዋል፤ ባለጸግነቱን በዐ መፅ የሚሰበስብ ሰው ገንዘቡ ከእ ርሱ ይቀማልና::

## አሥራ ዘጠነኛ አንቀጽ

ባሏ ስለሞተባትና ባልቴቶች የሚ ሰጣቸውን በምስጋና ይቀበሉ ዘንድ እንደሚገባ ይናገራል::

፩. እግዚአብሔር የሰጣቸውን በም ስጋና በፍርሃትና በመንቀጥቀጥ ይቀ በሉ ዘንድ፤ ለተራቡትም ምግብን የሚ ሰጥ እግዚአብሔርን ያመሰግኑት ዘንድ፤ ፈቲቱንና ባልቴቶችን እንምከራቸው::

፪. ከእናንተ ወገን በልክ የሚበላና የሚ ጠጣ ማነው? እጁን ዘርግቶ በፈቃዱ መልካሙን የሚያበዛ ለጐልማሶች ስን ዴውን ፤ ለደናግል ወይንን ፤ በሕይ ወት ለሚኖሩም የደስታ ዘይትን፤ ለእ ንስሳ ጥጋብን፤ ለአገልጋዮች ነፃነትን፤ ለአውሬዎች ሥጋን ፤ ለወፎችም ፍሬን፤ ለሁሉም እንደሚገባ ምግብን በፈቃዱ የሚሰጥ እግዚአብሔር የሰ ጠው አይደለምን::



፫. ወበእንተዝ ይቤ እግዚእነ ተመ ሰሉ በአዕዋፈ ሰማይ እለ ኢይዘ ርኡ ወኢየዐርሩ ወኢያስተጋብኡ ውስተ መዛግብት ወአቡክሙ ሰማ ያዊ ይሴስዮሙ ፈድፋደ ትኄይሱ አንትሙ አምብዙኅ አዕዋፍ::

፬. ኢተሐልዩ እንዘ ትብሉ ምንተ ንበ ልዕ ወምንተ ንሰቲ ወምንተ ንትከ ደን እስመ የአምር አቡክሙ ዘበሰ ማያት ከመ ተኃሥሡ ዘንተ ኵሎ::[፫]

፭. ወእመሰ ትፈቅዱ ትንሥኡ ሠናይቶ ወትረሱ መንግሥቶ አዕርጉ ሎቱ ስብሐተ ወበረከተ ወአኰቴተ ::

፮. ወለእለሰ ይትዌከፉ ዕቤረ ወዕጓለ ማውታ ያስተፌሥሖሙ እግዚአብ ሔር አብ በመንግሥተ ሰማያት በወ ልዱ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ሎቱ ክብር ወስብሐት ለዓለመ ዓለም አሜን::

## አንቀጽ ፳

በእንተ ከመ መፍትው ኤጲስ ቆጶስ ይለቡ ነሢአ መባእ በኀበ እለ ይደሉ::

፩. ተዓቀቡ እንከ እመያሲ እስመ ርኁቅ ድኅነቱ እምኀጢአት::

፪. ወበእንተዝ ይቤ ኢሳይያስ "አሌ ሎሙ" ለእለ ይቶስሑ ማየ ምስለ ወይን::[፩]

፫. ማቴ. ፮፥ ፳፭—፴፪
፩. ኢሳ. ፭፥፳፫

፫. ስለዚህም ጌታችን እንዲህ አለ፤ የማይዘሩ የማያጭዱና የማይሰበ ስቡ፤ ነገር ግን ሰማያዊ አባታችሁ የሚመግባቸው የሰማይ ወፎችን ምሰሉ ፤ ከብዙ ወፎች ይልቅ እናንተ ትበልጣላችሁ::

፬. ምን እንበላለን፤ ምን እንጠጣለን፤ ምንስ እንለብሳለን ብላችሁ አት ጨነቁ፤ ሰማያዊ አባታችሁ ይህን ሁሉ እንደምትሹ ያውቃልና::

፭. በጎውን ነገር ትቀበሉ ዘንድ፤ መን ግሥቱንም ትወርሱ ዘንድ ብትወዱ ግን ክብርንና ፍጹም ምስጋናን ለእርሱ አቅርቡ::

፮. ባልቴቷንና ድሀ አደጉን ለሚ ቀበሉ ግን እግዚአብሔር አብ በልጁ በኢየሱስ ክርስቶስ በመንግሥተ ሰማ ያት ደስ ያሰኛቸዋል፤ ክብርና ምስ ጋና ለእርሱ ይሁን፤ ለዘለዓለሙ አሜን::

## ሀያኛ አንቀጽ፤

ኤጲስ ቆጶሱ መስጠት ከሚገባቸው ሰዎች መባ መቀበልን ያስተውል ዘንድ እንደሚገባ ይናገራል::

፩. ከመሸተኛ መባን እንዳትቀበሉ ተጠንቀቁ፤ ከኃጢአት መዳኑ እጅግ የራቀ ነውና::

፪. ስለዚህም ኢሳይያስ እንዲህ አለ፤ ውሃን ከወይን ጋራ ለሚቀላቅሉ ሰዎች ወዮላቸው::

፫. ንርኀቅ እምስካር ወዝሙት እስመ ይቤ እግዚአብሔር አምላክ ኢታብኡ መባአ እምዐስበ ዝሙት።[፪]

፬. ተዓቀቡ እመሰጥ ወእለ ይሌቅሐ ንዋዮሙ በርዴ ወእምግሙናነ መንፈስ፣ ወግብረ እለ ይገብሩ ከመዝ ኢኮነ ሥሙረ በኀበ እግዚአብሔር።

፭. መፍትው ለኤጲስ ቆጶስ ይርኀቅ እምእለ ይትዔገልዎሙ ለዕቤራት ወለእጓለ ማውታ፣ ወእምእለ ይመልዑ ቤተ ሞቅሕ ንጹሓነ እለ አልቦሙ አበሳ፣ ወእምእለ ያከብዱ ዲበ አግብርቲሆሙ ቅኔ እኩየ ወይኄንንዎሙ በረኃብ ወበጽምዕ።

፮. ወለእለ ከመዝ ርኩስ መሥዋዕቶሙ ወኢትትመጠው እምኔሆሙ እስመ ምኑን በኀበ እግዚአብሔር ኵሉ ዘይገብር እኩየ ወይነብብ ዐመፃ።

፯. ንርኀቅ እምፈያት ወእመጠዓውያን ወእምእለ ይገብሩ ጣዖተ ወእመስሕታን ወእምእለ ይዔምፁ መዳልወ ወእምእኩያን መስተራትዓን ሐራ እለ ይበረብሩ ቤተ ነዳያን ወምስኪናን ወይመስጡ ንዋዮሙ በዐመፃ።

፫. ከሴሰኝነትና ከመስከር እንራቅ፣ ፈጣሪ እግዚአብሔር ከዝሙት ዋጋ መባ አትቀበሉ ብሏልና።

፬. ከቀማኞችና ገንዘባቸውን ባራጣ ከሚያበድሩ፣ ሰውነታቸውን ከሚያሳድፉ ሰዎች ተጠበቁ፣ እንዲህ የሚያደርጉ ሰዎች ሥራም በእግዚአብሔር ዘንድ የተወደደ አይደለም።

፭. ለኤጲስ ቆጶስ ባልቴቶችንና ድሃ አደጎችን ከሚነጥቁ፣ ንጹሓን ሰዎችንም በእስር ቤት ከሚያከማቹ፣ በአገልጋዮቻቸው ላይም ክፉ አገዛዝን ከሚያጸኑ፣ በረኃብና በጽምዕ ከሚገዟቸው ይርቅ ዘንድ አገባብ ነው።

፮. እንደዚህ ያሉት ሰዎች መሥዋዕታቸው ርኩስ ነው፣ ከእነርሱም አትቀበል፣ ክፉ የሚሠራና ዐመፅን የሚናገር ሁሉ በእግዚአብሔር ዘንድ የተናቀ ነውና።

፯. ከወንበዴዎች፣ ጣዖትን ከሚያመልኩ፣ ጣዖትንም ከሚሠሩ፣ ሰውን ከሚያስቱ፣ ሚዛኖችን ከሚያሳብሉ፣ የድሆችንና የችግረኞችን ቤት ከሚዘርፉ፣ ገንዘባቸውንም በዐመፅ ከሚነጥቁ ከክፉዎች ጭፍራዎች እንራቅ።

፪ ዘዳግ. ፳፫+፲፰



፰. ተዓቀቡ እንከ እምቀተልት ወእምጸናሕያነ ፍኖት ወእምዕልዋን ወእምእለ ይነሥቱ ሠናየ ምግባረ ወእምሰብእ ርኩሳን ወእምሰካርያን ወእምፀረፍት ወፈድፋደሰ እምእለ ይነሥኡ ርዴ።

፱. እስመ እሉ መስተቃርናቲሁ ለእግዚአብሔር እስመ ጽሑፍ ዘይብል "ጸላእከ እግዚኦ ኵሎሙ ገበርተ ዐመፃ ወትገድፎሙ ለኵሎሙ እለ ይነቡ ሐሰተ"።[፫]

፲. ወዘሰ ይጼዕል ወኢይሴሲ ዕቤረ ወዕጓለ ማውታ ይትኴነን በኀበ እግዚአብሔር፣ እስመ ዘገብረ አዶንያስ ነቢይ ጽሑፍ ውስተ መጽሐፈ ነገሥት ዘከመ ዐለዎ ለእግዚአብሔር ወበልዐ ኅብስተ ወሰትየ ማየ በመካን ዘአዘዞ እግዚአብሔር ኢይብላዕ በውስቴቱ በእንተ ዕልወተ ኢዮርብአም ወልደ ናባጥ ወበእንተዝ ቀተልዎ።[፬]

፲፩. ወዘይጼጽሙ በእንተ ሲሳየ መበለት እመኒ ብዙኀ አው ኅዳጥ ሥሙር በኀበ እግዚአብሔር ዘኢኮነ በዐመፃ።

፲፪. እስመ ጽሑፍ ዘይብል "ይኄይስ ኅዳጥ ዘበጽድቅ እምብዙኀ ብዕሎሙ ለኃጥአን"።[፭]

፰. እንግዲህ ከነፍሰ ገዳዮች፣ ከሸማቂዎች ፣ ከወንጀለኞች ፣ መልካሙን ሥራ ከሚያፈርሱ ከርኩሳን ሰዎች፣ ከሰካራሞች፣ ከተሳዳቢዎች፣ ይልቁንም አራጣ ከሚቀበሉ ሰዎች ተጠበቁ።

፱. እነዚህ የእግዚአብሔር ተቃራኒዎች ናቸውና፣ አቤቱ በደልን የሚሠሩ ሰዎችን ሁሉ ጠላህ ሐሰትንም የሚናገሩ ሰዎችን ትጥላቸዋለህ የሚልም ተጽፎአልና ።

፲. ባልቴትንና እናት አባት የሞቱበትን የማይመግበውን የሚሰድብ ሰው በእግዚአብሔር ዘንድ ይፈረድበታል፣ ነቢዩ አዶንያስ ያደረገው እግዚአብሔርንም እንደከዳ፣ ስለናባጥ ልጅ ስለ ኢዮርብአም ወንጀል በውስጡ እንዳይበላና እንዳይጠጣ እግዚአብሔር ባዘዘው ቦታ እንጀራ እንደበላና ውሀ እንደጠጣ ስለዚህም እንደገደሉት በነገሥት መጽሐፍ ተጽፏልና።

፲፩. ብዙም ቢሆን ጥቂትም ቢሆን በዐመፅ ያይደለ ስለ ባልቴቲቱ ምግብ የሚደክም በእግዚአብሔር ዘንድ የተወደደ ነው።

፲፪. ከብዙ የኃጢአተኞች ሀብት ጥቂት የጻድቃን ሀብት ይበልጣል የሚል ተጽፏልና።

፫. መዝ. ፭+፯
፬. ፩ኛ ነገሥ. ፲፫+፳፫
፭. መዝ. ፴፮+፲፯

፲፫. ወእመሰ በልዐት መበለት ወጸግበት በኀበ ዕልዋን ወጸለየት በእንቲአሆሙ ኢይሰምዕ እግዚአብሔር ጸሎታ።

፲፬. እስመ ይፈትን እግዚአብሔር ልበ ወኵልያተ[፮] እስመ ይቤ እግዚአብሔር በእንተ ዕልዋን ወመናፍቃን እመ ቆሙ ሙሴ ወሳሙኤል ወጸለዩ ኀቤየ ኢይሰምዕ ጸሎቶሙ ወኢይሠሪ ኃጢአቶሙ።

፲፭. ወአኮ በእንተ እሉ ባሕቲቶሙ አላ ባዕዳንሂ እለ አበሱ ወአበዩ ተመይጦ ውስተ ንስሓ።

፲፮. ወእምከመ ተመይጡ እሣሃሎሙ ወእሰምዕ ጸሎቶሙ።

፲፯. ወእለሰ ያምዕዕዎ ለእግዚአብሔር ወኢይዜከሩ እከየ ምግባሮሙ ይርኅቁ እንከ እምዘ ከመዝ ግብር እስመ ኵሎሙ እለ ኢይገብሩ ዘንተ ውፁአን እምሕግ።

፲፰. እስመ ኢተወክፈ ኤልሳዕ መሥዋዕተ አዛሄል ዘነግሠ ላዕለ ሶርያ አኪያ ያሠኒ መሥዋዕተ ኢዮርብአም።[፯]

፲፱. ወእመሰ ነቢያተ እግዚአብሔር ኢተወክፉ መባአ እምኀበ ዕልዋን ከማሁ ኤጲስ ቆጰሳት ርቱዕ ይፍርሁ ገቢረ ከመዝ።

፲፫. ባልቴቲቱ በወንጀለኞች ዘንድ ብትበላና ብትጠግብ ስለ እነርሱም ብትጸልይ እግዚአብሔር ጸሎቷዋን አይሰማም።

፲፬. እግዚአብሔር ልብንና ኵላሊትን መርምሮ ያውቃልና እግዚአብሔር ስለ መናፍቃንና ወንጀለኞች እንዲህ ብሏል፣ ሙሴና ሳሙኤል ቁመው ወደኔ ቢጸልዩ ጸሎታቸውን አልሰማም፣ ኃጢአታቸውንም አላስተሠርይላቸውም።

፲፭. ስለ እነዚህም ብቻ አይደለም ነገር ግን በንስሓም ስለ በደሉ መመለስን እንቢ ስላሉ ስለ ሌሎችም ነው።

፲፮. ቢመለሱ ግን ይቅር እላቸዋለሁ ጸሎታቸውንም እሰማለሁ።

፲፯. እግዚአብሔርን የሚያሳዝኑት የሥራቸውንም ክፋት የማያስቡ ከእንደዚህ ያለው ሥራ ይራቁ፣ ይህን የማያደርጉ ሁሉ ከሕግ የወጡ ናቸውና።

፲፰. ኤልሳዕ በሶርያ የነገሠ የአዛሄልን ስጦታ አልተቀበለምና አኪያም የኢዮርብአምን ስጦታ አልተቀበለምና።

፲፱. የእግዚአብሔር ነቢያት ከወንጀለኞች መባ ካልተቀበሉ እንደዚሁም ኤጲስ ቆጰሳት እንደዚህ ማድረግን ይፈሩ ዘንድ ይገባል።

፮. መዝ. ፯፥፲
፯. ፪ኛ ነገ. ፰ ፥ ፱-፲



፳. ወሲሞንሂ መሠርይ አምጽአ ኀቤነ ኀልያነ ለነ ለጴጥሮስ ወዮሐንስ ወመከረ ይንሣእ ክብረ ዘመልዕልተ ኵሉ ክብር ወንሕነሰ ኢነሣእነ እምኔሁ ኀልያነ አላ አሰርናሁ በማእሰር ዘለዓለም።[፳]

፳፩. ወውእቱሰ ፈቀደ ይምሥጥ ክብረ ዘኢተውህበ ሎቱ እምኀበ እግዚአብሔር ።

፳፪. ረኀቁኬ እምርኩስ መሥዋዕት ዘያበውኡ ቤተ እግዚአብሔር።

፳፫. ወካዕበ ይቤ ሰስሉ እምዐመፃ በፍርሀት ወበረዓድ።

፳፬. ወእመሰ ትብሉ እምኢነሣእነ መባዓ እምኀበ ዕልዋን ምንተ ንጼጉ ለዕቤራት ወለዕጓለ ማውታ ወለጽኑሳን እለ አልቦሙ ሲሳይ ወእመሰ ገበርክሙ ከመዝ ይከውነክሙ ኀጢአተ።

፳፭. እስመ ሠርዐ ለክሙ እግዚአብሔር በከመ ትካት ሌዋውያን ያነሥኡ መባዓ በኀበ ሕዝብ።

፳፮. ወእመሰ ዝንቱ ኵሉ ዘተሠርዐ ለቤተ ክርስቲያን ኢአከለክሙ መፍትው ትትዐገሡ ወትንበሩ በረኃብ ወበጽምዕ እምትንሥኡ

፳. ባለ ሥራዩ ሲሞንም ወደእኛ ወደ ጴጥሮስና ወደ ዮሐንስ መማለጃን አምጥቶ ከሁሉ ክብር በላይ የሚሆን ክብርን ይቀበል ዘንድ መከረ፣ እኛ ግን መማለጃን ከእርሱ አልተቀበልንም፣ ነገር ግን ለዘለዓለም በሚሆን ማሠሪያ አሠርነው እንጂ።

፳፩. እሱስ ከእግዚአብሔር ዘንድ ያልተሰጠውን ክብር ነጥቆ ሊወስድ ወዶ ነበረ።

፳፪. ወደ እግዚአብሔር ቤት ከሚያገቡት ከርኩስ መሥዋዕት ራቁ።

፳፫. ዳግመኛም በመፍራትና በመንቀጥቀጥ ከግፍ ራቁ አለ።

፳፬. ነገር ግን ከወንጀለኞች ዘንድ መባን ካልተቀበልን ለባልቴቶችና ለድሃ አደጎች ምግብ ለሌላቸው ችግረኞችም ምን እንሰጣለን ብትሉ፣ እንደዚህም ብታደርጉ፣ ኃጢአትን ይሆንባችኋል።

፳፭. ቀድሞ ሌዋውያን ከሕዝቡ ዘንድ መባን ይቀበሉ እንደነበር እግዚአብሔር ሠርቶላችኋልና።

፳፮. ለቤተ ክርስቲያን የተሠራው ይህ ሁሉ ባይበቃችሁ ግን እግዚአብሔርን ከሚጠሉ ሰዎች መባን ተቀብላችሁ መሳቂያና መዘበቻ ከም

፳ የሐዋ ሥራ ፰፥፲፰-፳፬

መባዓ በኀበ ጸላእያነ እግዚአብ ሔር ወትኩኑ ሰሐቀ ወስላቀ ወበእንተ እሉ ይቤ ነቢይ ወቅብዐ ኃጥአንሰ ኢይትቀባዕ ርእስየ።[፱]

፳፯. ተዐቀቡ ትንሥኡ መባዓ በኀበ እለ ይገብሩ ሠናየ ወበኀበ ዕልዋ ንሰ ኢትንሥኡ።

፳፰. ወእመሰ ጽኑስ አንተ ንግ ሮሙ ለመሃይምናን አኀው መፍ ቀርያነ እግዚአብሔር የሀቡ ጻሕ ቀከ።

፳፱. ወእምዘ ነሣእከ እምኔሆሙ ጸጉ ለዕቤራት ወለዕጓለ ማውታ በጽድቅ ።

፴. ይቤ ሰሎሞን ለሕዝብ ሀብ እምፃማከ በጽድቅ ከመ ይምላዕ ውስተ መዛግብቲከ ሥርናይ ወይ ምላዕ ምክያደ ወይንከ።[፲]

፴፩. እምፃማ መሃይምናን አልብ ስዎሙ ለዕሩቃን፤ ወተወከፍዎሙ እመባዕ ዘያቀርቡ ኀቤክሙ ወተ ቀነዩ ሎሙ በከመ ሥርዐተ ቅዱ ሳን።

፴፪. ወተቤዘውዎሙ ለፂውዋን፤ ወሐውጽዎሙ ለሙቁሓን፤ ወአን ግፍዎሙ ለቅቱላን፤ ከመ ትርከቡ ሕይወተ በኀበ እግዚአብሔር።

ትሆኑ ታገኛችሁ በመራብ በመጠ ማት ትኖሩ ዘንድ አገባብ ነው፤ ስለነዚህም ነቢዩ የኃጥአንን ዘይት ራሴን አልቀባም ብሏል።

፳፯. በጎ ሥራን ከሚያደርጉ መባን ትቀበሉ ዘንድ ተጠንቀቁ፤ (ተገቢ ነው) ከወንጀለኞች ግን አትቀበሉ።

፳፰. ችግረኛ ብትሆን ግን ግዳጅ ህን ይሰጡህ ዘንድ እግዚአብሔ ርን ለሚወዱ ወንድሞች ምእመ ናን ንገራቸው።

፳፱. ከእነርሱ ከተቀበልከውም ለባ ልቴቶችና ለድኃ አደጎች በእውነት ስጥ።

፴. ሰሎሞን እንዲህ አለ፤ እህል በጎተራህ ይሞላ ዘንድ፤ የወይንህ መጥመቂያ ይትረፈረፍ ዘንድ ከድ ካምህ በእውነት ለሕዝብ ስጥ።

፴፩. ምእመናን ከደከሙበት የታረ ዙትን አልብሷቸው፤ ወደናንተ ከሚ ያቀርቡት መባም ተቀበሏቸው፤ እንደ ቅዱሳን ንጹሓን ክቡራን ሥርዓትም አገልግሏቸው።

፴፪. በእግዚአብሔር ዘንድ ሕይወ ትን ታገኙ ዘንድ ምርኮኞቹን ዋጇቸው፤ የታሠሩትንም ጠይቋቸው፤ ይሙት በቃ የተፈረደባቸውንም አስጥሏቸው ።

---

፱. መዝ. ፻፵፥፭
፲. ምሳ. ፫፥፱—፲



፴፫. ናሁኬ ንኤዝዘክሙ ኢትትልዉ ፍኖቶሙ ለዕልዋን ወለመናፍቃን ወኢትትወከፉ መሥዋዕቶሙ ወኢ ትንሥኡ ንዋዮሙ እስመ ድልው ውእቱ መብልዕ ለእሳት።

፴፬. ወኢትትሐወሉ ምስሌሆሙ እስመ ርኩስ መሥዋዕቶሙ ለኃጥ አን በቅድመ እግዚአብሔር ዘንተ ነገርናክሙ ኦ አኃው ለበቊዔተ ነፍስክሙ።

አንቀጽ ፳ ወ ፩

በእንተ ከመ መፍትው ይገሥጹ አበው ውሉዶሙ፤

፩. ወአንትሙኒ አበው መሀርዎሙ ለደቂቅክሙ ይዕቀቡ ትእዛዘ እግዚአ ብሔር ወይትልዉ ፍኖቶ ለክርስ ቶስ ወአዝዝዎሙ ይትመሀሩ ቅኔ እድ።

፪. ወኢይንበሩ ጽሩዓነ እስመ እሙ ንቱ የዐብዩ ልቦሙ ወይርኅቁ እም ገቢረ ሠናይ ።

፫. ወበእንተዝ ሕፅንዎሙ ወኢት መሀኩ ገሥጾቶሙ እስመ ኢይመ ውት ወልድ በተግሣጽ አላ ዳዕሙ ይድኅን እምኵነኔ።

፬. እስመ ይቤ ኢትምህክ በትረከ እምውሉድከ እስመ ሠናይ ተስፋ ውእቱ ወእምከመ ዘበጥኮ በበትር አድኀንከ ነፍሶ እሞት።

፴፫. የመናፍቃንንና የከሓዲዎችን ጐዳና እንዳትከተሉ፤ መሥዋዕታቸ ውንም እንዳትቀበሉ፤ ገንዘባቸውንም እንዳትወስዱ እነሆ እናዝዛችኋለን መብሉ ለእሳት የተገባ ነውና።

፴፬. ከነሱ ጋራም አትቀላቀሉ፤ በእግ ዚአብሔር ፊት የኃጢአተኞች መሥ ዋዕት የሚያፀይፍ ርኩስ ነውና፤ ወንድሞች ሆይ! ለነፍሳችሁ ረብህ ጥቅም በመሆኑ ይህን ነገርናችሁ።

ሀያ አንደኛ አንቀጽ

አባቶች ልጆቻቸውን ይመክሩ ዘንድ አገባብ እንደሆነ ይናገራል።

፩. እናንተም አባቶች የእግዚአብ ሔርን ትእዛዝ ይጠብቁ ዘንድ፤ የክ ርስቶስን ጐዳና ይከተሉ ዘንድ ልጆ ቻችሁን አስተምሯቸው፤ የእጅ ሥራንም ይማሩ ዘንድ እዘዟቸው።

፪. ሥራ ፈቶች ሁነው አይቀመጡ፤ ልባቸውን ያስታብያሉና ከመልካም ሥራም ይርቃሉና።

፫. ስለዚህም እነርሱን መገሠፅን ሳታዘኑ አሳድጓቸው፤ ልጅ በመገ ሠፅ አይሞትምና ከፍርድ ይድናል እንጂ ።

፬. ከልጆችህ ጨንገርን መጣል አትራራ ብሏል፤ በጎ አለኝታ ስለ ሆነ፤ በጨንገርም ብትመታው ነፍ ሱን ከሞት አዳንህ ብሏልና።

፭. ወንዲ ይቤ ዘኢይጌሥጽ ወልዶ አብድ ውእቱ፣ ዝብጦ ለወልድከ ወስትር ገበዋቲሁ እንዘ ንኡስ ውእቱ፣ ከመ ኢይኩን ዝሉፈ ወኢይርኀቅ እምኔከ።

፮. ወዘሰ ኢይሜህር ወኢይጌሥጽ ወልዶ ጸልአ መሀርዎሙኬ ለደቂቅክሙ ቃለ እግዚአብሔር ወገሥፅዎሙ በንእሶሙ በዐቢይ ተግሣፅ ከመ ይኩኑ ትሑታነ ወይትአዘዙ ለኵሉ ወመሀርዎሙ ጽሒፈ ወአንብቦ መጻሕፍት ቅዱሳት።

፯. ወኢትኅድግዎሙ ጽሩዐነ ይሕየዉ ከመ ኢይዕልዉ ትዛዘክሙ።

፰. ወኢታብሕዎሙ ቤተ መያሲ ይባኡ ከመ ኢይርስዑ ተግሣጸ ወኢይማስኑ በዝሙት።

፱. ወእመሰ ተሀከዩ አበዊሆሙ ምሂረ ወገሥጸ ይከውኑ ሱቱፋነ ውስተ ኀጢአት ምስለ ውሉዶሙ።

፲. ወእምከመ በጽሑ አምጣነ ውርዙት ያውስቡ አንስተ በንጹሕ ሰብሳብ ከመ ኢይጽብኦሙ ፍትወተ ዝሙት ወውርዙት ወኢይኩኖሙ ጌጋየ።

፲፩. ወበእንተዝ ይትኀሠሥ እግዚአብሔር ፍዳ ኀጢአት እምአበዊሆሙ በዕለተ ምጽአት።

፭. ዳግመኛም ልጁን የማይገሥጽ አባት አላዋቂ ነው ብሏልና፣ ልጅህን ምታው፣ ጕኖቹንም ሰንጥቀው ትንሽ ሳለ የሚሳደብ እንዳይሆን ካንተም እንዳይርቅ።

፮. ልጁን የማያስተምር የማይገሥፅ ጠላው ብሏልና፣ ለልጆቻችሁ የእግዚአብሔርን ቃል አስተምሯቸው፣ ለሁሉ ትሕትናን አድርገው ይታዘዙ ዘንድ በትንሽነታቸው በታላቅ ምክር ገሥጿቸው፣ ጽሕፈትን ቅዱሳት መጻሕፍትንም ማንበብን አስተምሯቸው።

፯. ሥራ ፈቶች ሁነው ይኖሩ ዘንድም አትተዉዋቸው፣ ትእዛዛችሁን እንዳያፈርሱ።

፰. ወደ መሸተኛ ቤትም ይገቡ ዘንድ አታሰናብቷቸው፣ ተግሣጽን እንዳይዘነጉ በመሰሰንም እንዳይጠፉ ።

፱. አባቶቻቸው ግን ማስተማርን መገሠጽን ቸል ቢሉ፣ በኃጢአት ከልጆቻቸው ጋራ ተባባሪዎችን ይሆናሉ።

፲. አካለ መጠንም ካደረሱ በንጹሕ ጋብቻ ሴቶችን ያግቡ፣ የጕልማስነትና የሴሰኝነት ፈቃድ እንዳይዋጋቸው፣ በደልም እንዳይሆንባቸው።

፲፩. ስለዚህ በዕለተ ምጽአት እግዚአብሔር ከአባቶቻቸው ፍዳ ኃጢአትን ይመራመራል።



አንቀጽ ፳ወ፪

በእንተ ከመ መፍትው ይትሐቱ አግብርት ለአጋእዝቲሆሙ በኵሉ ንጽሕ እመሂ ዕልዋን አው መሃይምናን፤

፩. ምንተ እንከ ትብሉ በእንተ አግብርት ይኩኑኬ ማእምራነ ወይትቀነዩ ለአጋእዝቲሆሙ በፈሪሀ እግዚአብሔር።

፪. ወእመሰ ገብር ክርስቲያናዊ ውእቱ ወእግዚኡ ዕልው ይትቀነይ ሎቱ መፍትው በኵሉ ግብር ወባሕቱ ኢይኅበር ምስሌሁ ሃይማኖተ።

፫. ወከማሁ አጋዕዝትኒ ያፍቅሩ አግብርቲሆሙ ።

፬. ወእመሰ ሊቁ ወእግዚኡ ምእመን ይትቀነይ ሎቱ ወይፍርሆ ከመ ዘእግዚአብሔር ወይረስዮ ከመ አብ ወከመ ሊቅ ኄር።

፭. ወበእንተዝ ይነሥእ ዕሤተ ሠናየ ህየንተ ዘተቀንየ ለእግዚኡ።

፮. ወእመቦ እግዚእ ዘቦቱ ገብር ምእመን ወይገብር ፈቃዶ ያፍቅሮ ከመ ወልዱ፣ ወይረስዮ ከመ እኁሁ፣ በእንተ ፍቅረ ሃይማኖት።

፯. ወተተሐቱ ወተአዘዙ ለነገሥት ወለመኳንንት ፈራህያነ እግዚአብሔር እስመ እሙንቱ ላእ[illegible]

ሀያ ሁለተኛ አንቀጽ

አገልጋዮች ለጌቶቻቸው ከሐዲዎችም ቢሆኑ፣ ምእመናንም ቢሆኑ፣ በፍጹም ንጽሕና ትሕትናን ያደርጉ ዘንድ እንዲገባ ይናገራል።

፩. ስለ አገልጋይ እንግዲህ ምን ትላላችሁ? አዋቆችን ሁነው እግዚአብሔርን በመፍራት ለጌቶቻቸው ይገዟቸው።

፪. አገልጋይ ክርስቲያን ቢሆን፣ ጌታው ከሐዲ ቢሆን፣ በሥራው ሁሉ ይገዛለት ዘንድ አገባብ ነው፣ ነገር ግን ከርሱ ጋራ በሃይማኖት አይተባበር።

፫. ጌቶችም እንደዚሁ አገልጋዮቻቸውን ይውደዱ።

፬. አለቃው (ጌታው) ክርስቲያን ቢሆን ግን ይገዛለት የእግዚአብሔርም አገልጋይ እንደመሆኑ ይፍራው፣ እንደ አባትም እንደ ቸር አለቃም ያድርገው።

፭. ስለዚህም ለጌታው ስለአገለገለ በጎ ዋጋን ይቀበላል።

፮. ፈቃዱን የሚሠራ ክርስቲያን አገልጋይ ያለው ሰው ቢኖር ስለ ሃይማኖት ፍቅር እንደ ልጁ ይውደደው፣ እንደ ወንድሙም ያድርገው።

፯. እግዚአብሔርን ለሚፈሩ ነገሥታት መኳንንትም ራሳችሁን ዝቅ አድርጋችሁ ታዘዙ፣ እነርሱ የእግዚአብሔር መልክተኞች ናቸውና።

፮. ፍርህዎሙ እንከ ለሥዩማን በከመ ይደሉ ወአቅርቡ ሎሙ እምዘ·በክሙ ለክብር ወበተአገዞ በከመ ሕገ እግዚአብሔር፡፡

፯. ወኢትግበሩ ለክሙ ምክንያተ አላ ዳዕሙ ተፋቀሩ በበይናቲክሙ በከመ አዘዘ እግዚአብሔር አም ላክ በወልዱ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ፡፡

## አንቀጽ ፷ወ፫

በእንተ ከመ ኢመፍትው ለደና ግል ይብፅዓ ርእሶን ዘእንበለ ያመ ክሪ ነፍሶን፡፡

፩. ኢመፍትው ይባኣ ውስተዝ ግብር ዘእንበለ ይትመከራ ወይዕ ቀባ ርእሶን በንጽሕ፡፡

፪. ወከመዝ ንኤዝዞን ኢይባኣ ፍጡነ ዘእንበለ ይብጻሕ አምጣኖን፡፡

፫. በከመ ይቤ ሰሎሞን ይኄይስ ኢበፂዕ እምይብፃዕ ወይግባእ፡፡

፬. ትኩን እንከ ድንግል ንጽሕተ በነፍስ ወበሥጋ ከመ ትኩን እንከ ቤቶ ለእግዚአብሔር ወማኅደሮ ለክርስቶስ ወምዕራፎ ለመንፈስ ቅዱስ፡፡

፭. ወትሑር በፍኖተ ስብከተ ወንጌል ወበትእዛዝ ዘያሠምሮ ለእግዚአብሔር ወኢይኩን ምግ ባሪ በከመ ሥርዐተዝ ዓለም፡፡

፮. እንግዲህ እንደሚገባ ሹማምን ትን ፍሯቸው፤ ካላችሁም እንደ እግዚአብሔርም ሕግ በማክበርና በመታዘዝ አቅርቡላቸው፡፡

፯. ለእናንተም ምክንያትን አታድ ርጉ፤ ነገር ግን ፈጣሪ እግዚአብ ሔር እንዳዘዘ በልጁ በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ እርስ በርሳ ችሁ ተፋቀሩ ፡፡

## ሃያ ሦስተኛ አንቀጽ

ደናግል ሰውነታቸውን ሳይፈትኑ ራሳቸውን ይሣሉ ዘንድ እንዳ ይገባ ይናገራል፡፡

፩. አመክሮ ሳያደርጉና ራሳቸውን በንጽሕና ሳይጠብቁ ወደዚህ ሥራ ይገቡ ዘንድ አገባብ አይደለም፡፡

፪. አካለ መጠንም ሳያደርሱ ፈጥ ነው ወደ ብፅዓት እንዳይገቡ እን ዲህ እናዝዛቸዋለን፡፡

፫. ሰሎሞን ተስሎ ካለማድረግ አለ መሳል ይሻላል እንዳለ፡፡

፬. እንግዲህ ድንግል ሴት ለእግዚ አብሔር ቤት ለክርስቶስ ማደሪያ ለመንፈስ ቅዱስ ማረፊያ ትሆን ዘንድ በነፍስም በሥጋም የነጻች ትሁን ፡፡

፭. በትምህርተ ወንጌል መንገድና እግዚአብሔርን ደስ በሚያሰኘው ትእዛዝ ጸንታ ትኑር፤ ሥራዋም እን ደዚህ ዓለም ሥርዓት አይሁን፡፡



፮. ወኢታንሶሱ ውስተ ሀገር ወኢ ትሑር ውስተ ፍናው እኩያት ወኢትኩን ዘ፪ልባ አላ ትኩን ጠባበ ወንጽሕተ ዘአልባ ነውር፡፡

፯. ወኢትፍቅድ ተወድሶ ወፈድፋ ደሰ ጽሩዐ ነገረ፡፡

## አንቀጽ ፷ ወ፬

በእንተ ሰማዕት እለ ወሰድዎሙ ኀበ ምኵናን ወያመነድብዎሙ በዐቢይ ኵነኔ በእንተ በዓላት ወፋሲካ፡፡

፩. እመቦ ክርስቲያናዊ ዘወሰድዎ ኀበ ምኵናነ ዕልዋን፤ እመሂ ለቀ ቲል፤ አው ለተሰዶ፤ እመሂ ለተሞ ቅሖ፤ አው የሀብዎ ለአራዊት በእ ንተ ስመ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስ ቶስ ወርትዕት ሃይማኖት ወፍቅረ እግዚአብሔር፤ ኢትሚጡ ገጸክሙ እምኔሁ፡፡

፪. ባሕቱ ፈንዉ ሲሳዮሙ እምን ዋይክሙ፡፡

፫. ወዓዲ ለእለ የዐቅብዎሙ መስ ተራትዓተ ሐራ ሀቡ ሲሳዮሙ ከመ ኢያክብዱ ፃዕረ ኵነኔ ላዕ ሌሆሙ፡፡

፬. ወኢትግድፍዎ ለክርስቲያናዊ እኁክሙ ዘሰሐብዎ ኀበ ዐውደ ምኵናን በእንተ ስመ እግዚአብሔር አምላክነ፡፡

፮. ወደ ከተማም አትመላለስ፤ በክ ፉዎች ጐዳናዎችም አትሂድ፤ ሁለት ልብም አትሁን፤ አዋቂ ነውር የሌለ ባትም ንጽሕት ትሁን እንጂ፡፡

፯. መመስገንን፤ ይልቁንም ፈራሽ ነገርን አትውደድ፡፡

## ሀያ አራተኛ አንቀጽ

ስለ በዐላትና ፋሲካ ወደ አደባባይ ወስደው በጽኑዕ መከራ ፍርድ የሚያስጨንቋቸው የሰማዕታትን ነገር ይናራል፡፡

፩. ስለ እግዚአብሔር ፍቅርና ስለ ቀናች ሃይማኖት፤ ስለ ጌታችን ኢየ ሱስ ክርስቶስ ስም፤ ለመታሠር ቢሆን፤ ለመሰደድም ቢሆን፤ በሰማ ዕትነት ለመገደልም ቢሆን፤ ለአራ ዊትም ይሰጡት ዘንድ ወደ ወንጀ ለኞች የፍርድ አደባባይ የወሰዱት ክርስቲያን ቢኖር፤ ፊታችሁን ከእ ርሱ አትመልሱ፡፡

፪. ከገንዘባችሁ ምግባቸውን ላኩላ ቸው እንጂ፡፡

፫. ዳግመኛም ለሚጠብቋቸው ጭፍ ሮች ምግባቸውን ስጡ፤ በእነርሱ ላይ መከራ እንዳያጸኑባቸው፡፡

፬. ስለ አምላካችን ስለ እግዚአብ ሔር ስም ወደ አደባባይ የሚጐት ቱት ክርስቲያን ወንድማችሁንም አትጣሉት፡፡

፭. ዝኬ ውእቱ ቅዱስ ሰማዕት አኀውሁ ለእግዚእነ ወወልዱ ለል ዑል ወማኅደሩ ለመንፈስ ቅዱስ።

፮. ዝውእቱ ምእመን ዘዐቀበ ትእዛዘ ወንጌል ወወረሰ አክሊለ ሕይወት ወኮነ ስምዐ በእንተ ሕማመ እግዚእነ ክርስቶስ ወፍቁር ለደሙ ክቡር።

፯. ወበእንተዝ ኦ መሃይምናን በዓ ማክሙ ወበንዋይክሙ ተቀነዩ ለቅዱሳን።

፰. ወእለሰ አልቦሙ ንዋይ ይጹሙ በእንቲአሆሙ ወእለሂ ቦሙ የሀቡ ክፍለ ንዋዮሙ ለቅዱሳን።

፱. ወእመሰቦ ዘይሁብ ኵሎ ንዋዮ ቤዛ በእንቲአሆሙ ከመ ያድኅኖሙ ዝኬ ብፁዕ ውእቱ ወዐርኩ ለክርስቶስ።

፲. ወእመሰቦ ዘይሁብ ኵሎ ንዋዮ ለነዳያን ይከውን ኅሩየ ወንጹሐ እፎኬ ፈድፋደ ዘይጼጉ ንዋዮ በእንተ ሰማዕት።

፲፩. ዝውእቱ ዘፈጸመ ሥምረቶ ለእግዚአብሔር ወተመሰሎሙ ለቅዱሳን እለ አምኑ በእግዚእነ በቅድመ አሕዛብ ወነገሥት ወሕዝበ እስራኤል።

፭. ይህ የጌታችን ወንድም፣ የልዑል ልጅ፣ የመንፈስ ቅዱስ ማደሪያ ቅዱስ ሰማዕት ነው።

፮. የወንጌልን ትእዛዝ የጠበቀ፣ የሕይወት አክሊልን የወረሰ፣ ስለ ጌታችን ክርስቶስ መከራ ምስክር የሆነ የክቡር ደሙም ወዳጅ የሆነ ምእመን ይህ ነው።

፯. ስለዚህም ምእመናን ሆይ በድካማችሁና በገንዘባችሁ ቅዱሳንን አገልግሉ።

፰. ገንዘብ የሌላቸው ግን ስለ እነርሱ ይጹሙ ገንዘብ ያላቸውም ከገንዘባቸው ከፍለው ለቅዱሳን ይስጡ።

፱. ከመከራ ያድናቸው ዘንድ ስለ እነርሱ ቤዛ አድርጐ ገንዘቡን ሁሉ የሚሰጥ እርሱ ብፁዕ ነው፣ የክርስቶስም ወዳጁ ነው።

፲. ገንዘቡን ሁሉ ለነዳያን የሚሰጥ ሰው ቢኖር የተመረጠና ንጹሕ ከሆነ ስለ ሰማዕታት ገንዘቡን የሰጠ እንደ ምን ይሆን?

፲፩. የእግዚአብሔርን ፈቃድ የፈጸመ ይህ ነው፣ በአሕዛብ በነገሥታትና በእስራኤል ሕዝብ ፊት በጌታችን ያመኑ ቅዱሳንን መሰላቸው።



፲፪. እስመ ይቤ ዘሰ አምነኒ በገጸ ሰብእ አነኒ አአምኖ በገጸ አቡየ ዘበሰማያት[፩]፣ ወለእለሰ ይገብሩ ከመዝ ይከውኖሙ ስምዐ ክርስቶስ በኀበ አብ።

፲፫. ወአንትሙሰ ኢኮነ ርቱዐ ትትሐከዩ ወትኅፈሩ ሐዊረ ቤተ ሞቅሕ ተሐውጽዎሙ ለሙቁሓን አላ ዳዕሙ ርድዕዎሙ ወና ዝዝዎሙ።

፲፬. ወእምከመ ዘንተ ገበርክሙ ትትኄለቁ ምስለ ሰማዕት እስመ ለእሙንቱ ተጽሕፈ ስምዖሙ በእንተ ዘሐሙ ወተመንደቡ።

፲፭. ወአንትሙኒ ተኆለቍሙ ምስሌሆሙ በእንተ ዘተቀነይክሙ ሎሙ በጥቡዕ ልብ ወበሠናይ መልእክት ዘእንበለ ሐኬት።

፲፮. ወበእንተ እሉ ይቤ እግዚእነ ንዑ ኅቡየ ቡሩካኑ ለአቡየ ትረሱ መንግሥተ ሰማያት ዘድልው ለክሙ እምቅድመ ይትፈጠር ዓለም።

፲፯. እስመ ርኅብኩ ወአብላዕክሙኒ፣ ጸማዕኩ ወአስተይክሙኒ፣ ነግደ ኮንኩ ወተወከፍክሙኒ፣ ዐረቁ ወአልበስክሙኒ፣ ደወይኩ ወሐወፅክሙኒ፣ ተሞቃሕኩ ወነበብክሙኒ።

፩. ማቴ. ፲፥፴፪

፲፪. በሰው ፊት ያመነኝን ሰው እኔም በሰማያዊ አባቴ ፊት አምነዋለሁ ብሏልና፣ እንደዚህ ለሚሠሩት ክርስቶስ በአብ ዘንድ ምስክርን ይሆናቸዋል።

፲፫. እናንተ ግን የታሠሩትን ለመጐብኘት ወደ እሥር ቤት መሄድን ቸል ትሉና ታፍሩ ዘንድ የተገባ አይደለም፣ እርዷቸው አጥናኗቸው እንጂ።

፲፬. ይህን ብታደርጉ ከሰማዕታት ጋራ ትቆጠራላችሁ መከራን ስለ ተቀበሉ፣ ስለ ተጨነቁም ምስክርነታቸው ተጽፏልና።

፲፭. እናንተም በቈራጥ ልብና በመልካም አገልግሎት እነርሱን ያለ ስንፍና ስለ አገለገላችሁ ከእነርሱ ጋራ ተቆጥራችኋል።

፲፮. ስለእነዚህም ጌታችን እንዲህ አለ፣ ዓለም ሳይፈጠር የተዘጋጀላችሁን መንግሥተ ሰማያትን ትወርሱ ዘንድ የአባቴ ቡሩካን ወደኔ ኑ።

፲፯. ብራብ አብልታችሁኛልና፣ ብጠማም አጠጥታችሁኛልና ፣ እንግዳ ብሆን ተቀብላችሁኛልና ፣ ብታረዝ አልብሳችሁኛልና፣ ብታመም ጐብኝታችሁኛልና፣ ብታሠር ጠይቃችሁኛልና።

፲፰. ወአሜሃ ያወሥኡ ጻድቃን ወይብሉ እግዚኦ ማዕዜኑ ርኢናከ ርኁበከ ወአብላዕናከ፣ ጽሙዓከ ወአስተይናከ፣ ማዕዜኑ ርኢናከ እን ግዳከ ወተወከፍናከ፣ ወዕሩቀከ ወአ ልበስናከ፣ ወድውየከ ወሐወጽናከ፣ ወሙቁሐከኒ ወነበብናከ።

፲፱. ወያወሥእ ንጉሥ ወይብ ሎሙ አሜን እብለክሙ ኵሎ ዘገ በርክሙ ለአሐዱ እምእሉ ንዑሳን አኃውየ እለ የአምኑ ብየ ሊተ ገበር ክሙ።

፳. ወእምዝ ይብሎሙ ለእለ በጸ ጋሙ ሑሩ እምኔየ ርጉማን ውስተ እሳት ዘለዓለም ዘድልው ለሰይ ጣን ወለመላእክቲሁ።

፳፩. እስመ ርኅብኩ ወኢያብላዕ ክሙኒ፣ ጸማዕኩ ወኢያስተይክ ሙኒ፣ ነግደ ኮንኩ ወኢተወከፍክ ሙኒ ፣ ዐረቁ ወኢያልበስክሙኒ፣ ደወይኩ ወኢሐወጽክሙኒ ተሞቃ ሕኩ ወኢነበብክሙኒ።

፳፪. አሜሃ ያወሥኡ እለ በፀ ጋሙ እንዘ ይብሉ እግዚኦ ማዕ ዜኑ ርኢናከ ርኁበከ ወጽሙዓከ ወእንግዳከ ወዕሩቀከ ወድውየከ ወተሞቂሐከ ወኢተልእክናከ።

፲፰. ያን ጊዜም ጻድቃን እንደዚህ ብለው ይመልሳሉ፣ አቤቱ መቼ ተር በህ አይተንህ አብልተንህ፣ መቼስ ተጠምተህ አይተንህ አጠጥተንህ፣ መቼ እንግዳ ሁነህ አይተንህ ተቀብ ለንህ፣ መቼ ታርዘህ አይተንህ አል ብሰንህ፣ መቼ ታመህ አይተንህ ጐብ ኝተንህ፣ መቼ ታሥረህ አይተንህ ጠይቀንህ፣ ብለው ይመልሱለታል።

፲፱. ንጉሡም እንደዚህ ብሎ ይመ ልስላቸዋል፣ ከእነዚህ በእኔ ከሚያ ምኑ ከታናናሾቹ ወንድሞቼ ላንዱ ያደረጋችሁትን ለእኔ አደረጋችሁ ብዬ በእውነት እነግራችኋለሁ።

፳. ከዚህ በኋላ በግራ ያሉትን እና ንተ የተረገማችሁ ከኔ ሒዱ ለዲያብ ሎስና ለሠራዊቱ ወደ ተዘጋጀ የዘለ ዓለም እሳት ሂዱ ይላቸዋል።

፳፩. ብራብ አላበላችሁኝምና፣ ብጠማ አላጠጣችሁኝምና፣ እንግዳ ብሆን አል ተቀበላችሁኝምና፣ ብታረዝ አላለበሳ ችሁኝምና፣ ብታመም አልጐበኛችሁ ኝምና ፣ ብታሠር አልጠየቃችሁ ኝምና።

፳፪. ያን ጊዜም በስተግራ ያሉት አቤቱ ተርበህ አይተንህ ያላበላንህ፣ ተጠም ተህ አይተንህ ያላጠጣንህ፣ እንግዳ ሁነህ መጥተህ ያልተቀበልንህ፣ ታር ዘህ አይተንህ ያላለበስንህ፣ ታመህ አይ ተንህ ያልጠየቅንህ፣ ታሥረህ አይተ ንህ ያልጐበኘንህ መቼ ነው? እያሉ ይመልሱለታል።



፳፫. ወእምዝ ያወሥኦሙ ንጉሥ እንዘ ይብል አሜን እብለክሙ ዘኢገበርክሙ ለአሐዱ እምእሉ ንኡ ሳን ሊተ ኢገበርክሙ።

፳፬. ወየሐውሩ እሉሂ ውስተ ኵነኔ ዘለዓለም።

፳፭. ወጻድቃንሰ ውስተ ሕይወት ዘለዓለም።[፩]

፳፮. እመቦ ዘይብል ክርስቲያናዊ አነ ወይገብር እኩየ ይዜሙ ወይ ረኵስ ይፍትሑ ላዕሌሁ ፍትሐ ቀትል ወእምዝ ከመዝ ብእሲ ረኀቁ እምኔሁ።

፳፯. ኢመፍትው ለክርስቲያን ይኩኑ ውፁኣነ እምሕግ ወይፍ ትሑ በገቢረ እኩይ።

፳፰. አላ ይትገሐሡ እምዕልዋን ወመናፍቃን ወኢይኅበሩ ምስ ሌሆሙ።

፳፱. ወእምዕልዋን እለ ይሞቅሕ ዎሙ ለክርስቲያን ወየአስርዎሙ ወይሜጥውዎሙ ለቀቲል በእንተ ስመ ክርስቶስ ተዐቀቡ።

፴. ወአድኅኑ አኀዊክሙ ወአባ ለክሙ እምእደዊሆሙ ለዕልዋን።

፴፩. ወእመቦ ክርስቲያናዊ ዘጻመወ በእንቲአሆሙ ብፁዕ ውእቱ ወይ ትኌለቍ ምስለ ሰማዕት እስመ ሐመ በእንተ ክርስቶስ።

[illegible]

፳፫. ከዚህም በኋላ ንጉሡ ከእነ ዚህ ከታናናሾቹ ለአንዱ ያላደረ ጋችሁት ለእኔ አለማድረጋችሁ ነው ብሎ ይመልስላቸዋል።

፳፬. እነርሱም ወደዘለዓለም ፍርድ ይሄዳሉ።

፳፭. ጻድቃን ግን ወደዘለዓለም ሕይወት ይሄዳሉ።

፳፮. እኔ ክርስቲያን ነኝ የሚል ክፉ ሥራን የሚሠራ፣ የሚሰስንና የሚ ረክስ ሰው ቢኖር፣ የሞት ፍርድን ይፍረዱበት፣ እንደዚህ ካለው ሰው ራቁ ።

፳፯. ክርስቲያኖች ከሕግ የወጡ ሊሆኑና ክፉ በመሥራት ሊፈ ርዱ አገባብ አይደለም።

፳፰. ነገር ግን ከወንጀለኞችና ከመ ናፍቃን፣ ይለዩ፣ ከእነርሱም ጋራ አንድ አይሁኑ።

፳፱. ስለ ክርስቶስ ስም ክርስቲያ ኖችን ወደ ግዞት ቤት ከሚያገቡ አስረውም ለሞት አሳልፈው ከሚ ሰጡ ከሓድያን ተጠበቁ።

፴. ወንድሞቻችሁንና ሰውነታችሁን ከከሐድያን እጅ አድኑ ።

፴፩. ስለነርሱም የደከመ የክር ስቲያን ወገን ቢገኝ ብፁዕ ነው፣ ከሰማዕታት ጋራ ይቆጠራል፣ ስለ ክርስቶስ መከራን ተቀብሏልና።

፴፪. ወከማሁ ለነኒ ረከበነ ሕማም ወምንዳቤ በኀበ ቀያፋ ወእለእስክንድሮስ ወሐና እሉ እሙንቱ ሊቃነ ካህናት::

፴፫. ወእምዝ ወፃእነ እምኔሆሙ እንዘ ንትፌሣሕ እስመ ኮነ ድልዋነ ንፁር ሕማማቲሁ ለክርስቶስ::

፴፬. ወከማሁ አንትሙኒ ተዐገሡ ወተፈሥሑ በእንተ ሕማም ከመ ትኩኑ ብፁዓነ በይእቲ ዕለት::

፴፭. ወለእለሰ ይሰድድዎሙ በእንተ ሃይማኖት ወይወፅኡ እምሀገር ለሀገር በትእዛዘ ወንጌል ዘእግዚእነ ተወከፍዎሙ ወአዕርፍዎሙ ወአኀድርዎሙ ኀቤክሙ ከመ ሰማዕት እንዘ ትትፌሥሑ እስመ ኮንክሙ አዕርክተ ምስሌሆሙ::

፴፮. ለብዉኬ ከመ ጽዉዓን እሙንቱ በኀበ እግዚአብሔር እስመ ይቤ እግዚእነ ብፁዓን አንትሙ ሶበ ይጼዕሉክሙ ወይዘነጕጉክሙ ወይነቡ ኵሎ እኩየ ላዕሌክሙ እንዘ ይሔስዉ በእንቲኣየ ተፈሥሑ ወተሐሠዩ እስመ አስብክሙ ብዙኅ ውእቱ በሰማያት::[፫]

፴፯. እስመ ከመዝ ሰደድዎሙ ለነቢያት እለ እምቅድሜክሙ::

፫. ማቴ. ፭፥፲፩-፲፪

፴፪. እንደዚሁም እኛን መከራና ጭንቅ በቀያፋ በእለ እስክድሮስና በሐና ዘንድ አግኝቶን ነበረ፤ እነዚህም የካህናት አለቆች ናቸው::

፴፫. ከዚህም በኋላ ደስ እያለን ከእነርሱ ዘንድ ወጣን፤ የክርስቶስን መከራዎች እንቀበል ዘንድ ዝግጁዎች ሁነናልና::

፴፬. እናንተም እንደዚሁ ታገሡ፤ በዚያችም ቀን ብፁዓን ትሆኑ ዘንድ ስለ መከራው ደስ ይበላችሁ::

፴፭. ስለ ሃይማኖትም የሚያሳድዱአቸውን ከሀገርም ወደ ሀገር የወጡትንም በጌታችን ወንጌል ትእዛዝ ተቀብላችሁ አሳርፏቸው፤ በናንተም ዘንድ ሰማዕት እንደ መሆናቸው ደስ እያላችሁ አሳድሩዋቸው ከእነርሱ ጋራ ወዳጆች ሁናችኋልና::

፴፮. እነዚህም በእግዚአብሔር ዘንድ ንው ኀቤየ ቡሩካን ለሕቡየ ተብለው የሚጠሩ እንደሆኑ አስተውሉ፤ ጌታችን ቢሰድቧችሁ ቢያሽሟጥጧችሁ በእኔም ምክንያት ክፉውን ሁሉ በሐሰት ቢናገሩአችሁ ብፁዓን ናችሁ፤ ዋጋችሁ በሰማያት ብዙ ነውና ደስ ይበላችሁ ብሏል::

፴፯. ከናንተ አስቀድመው የነበሩ ነቢያትን እንዲሁ ያሳድዷቸው ነበረና::



፴፰. ወዓዲ ይቤ እምከመ ኪያየ ሰደዱ ኪያክሙኒ ይሰድዱክሙ::

፴፱. ወካዕበ ይቤ ሶበ ይሰድዱክሙ እምውስተ ዛቲ ሀገር ጕዩ ውስተ ካልእታ::

፵. ወአንትሙ ተኀዝኑ ወትቴክዙ በውስተዝ ዓለም እስመ ያኀብኡክሙ ውስተ ማኅበር ወመኳንንቲሆሙ ወይቀሥፉክሙ ወኀበ መሳፍንት ወነገሥት ይወስዱክሙ በእንተ አየ ስምዕ::

፵፩. ወዘሰ አዝለፈ ትዕግሥቶ ውእቱ ይድኀን::[፬]

፵፪. ወዘሰ ይሰድድዎ በእንተ ስመ ክርስቶስ ወተዓገሦ ኮነ ሰማዕተ ውእቱኬ በአማን ብእሴ እግዚአብሔር::

፵፫. ወዘሰ ይትዓረክ ምስለ ዕልዋን ወክህዶ ለክርስቶስ ከመ ኢይጽልዕዎ መናፍቃን ወያበድር ርእሶ እምነ እግዚኡ ዘውስተ መንፈሱ ዝኬ ውእቱ ጽሉእ ወምኑን ወፅሩዕ በኀበ እግዚአብሔር::

፵፬. እስመ አብደረ ፍቅረ ሰብእ ወኮነ ጸላዒሁ ለእግዚአብሔር ወነሥአ ክፍለ ርጉማን ወአኮ ምስለ ቅዱሳን ወህየንተ መንግሥት ዘድሉት ለቡሩካን ኀረየ ሎቱ እሳተ ገሃነም ዘለዓለም ዘድሉት ለሰይጣን ወለመላእክቲሁ::

፬. ማቴ. ፲፥፲፱ – ፳፪

፴፰. ዳግመኛም እኔን ካሳደዱኝ እናንተንም ያሳድዷችኋል አለ::

፴፱. ሁለተኛም ከዚች አገር ቢያሳድዷችሁ ወደ ሌላይቱ አገር ሽሹ አለ::

፵. እናንተም በዚህ ዓለም ታዝናላችሁ ትተክዛላችሁ፤ ወደ ነገሥታትና ወደ ፈራጆቻቸውም አሳልፈው ይሰጡአችኋል፤ ይገርፏችኋል፤ ስለ እኔ ስለመሰከራችሁ ወደ መሳፍንትና ነገሥታትም ይወስዱዋችኋል ::

፵፩. መከራውን መታገሥ ያዘወተረ ግን እርሱ ይድናል::

፵፪. ስለ ክርስቶስ ስም የሚያሳድዱት ሰው መከራውን በታገሠ ጊዜ ሰማዕትን ሆነ፤ በእውነት የእግዚአብሔር ሰው እርሱ ነው::

፵፫. ከዐላውያን ጋር የሚወዳጅ መናፍቃን እንዳይጠሉት ክርስቶስን የሚክድና በልቡናው ውስጥ ከአለው ከጌታው ይልቅ ራሱን የሚያስቀድም ግን እርሱ በእግዚአብሔር ዘንድ የተጠላ የተናቀና የጠፋ ነው::

፵፬. የሰውን ፍቅር መርጦ የእግዚአብሔር ጠላት ሁኗልና፤ የርጉማንን እድል አግኝቷልና ከቅዱሳን ጋርም አይደለም፤ ለቡሩካን ጻድቃን በተዘጋጀችው መንግሥት ፈንታ ለሰይጣንና ለሠራዊቱ የተዘጋጀች የዘለዓለም እሳት ገሀነምን ለራሱ መርጦአልና::

፵፭. ወበእንተዝ አውሥአ እግዚ
እነ ወይቤ ወዘሰ ክህደኒ በገጸ
ሰብእ አነኒ እክህዶ በገጸ አቡየ
ዘበሰማያት::

፵፮. ወካዕበ አዘዘ እንዘ ይብል
ዘያፈቅር አበ ወእመ እምኔየ ኢይ
ደሉ ሊተ፤ ወዘያፈቅር ወልዶ ወወ
ለቶ እምኔየ ኢይደሉ ሊተ::

፵፯. ወዘሰ ኢነሥአ መስቀለ
ሞቱ ወኢተለወ ድኅሬየ ኢይደሉ
ሊተ::

፵፰. ወዘረከባ ለነፍሱ ለይግ
ድፋ ወዘገደፋ ለነፍሱ በእንቲ
አየ ይረክባ::

፵፱. ምንት ይበቁዖ ለሰብእ
ለእመ ኰሎ ዓለመ ረብሐ ወነፍሶ
ኀጕለ ወምንተ እምወሀበ ቤዛ
ለነፍሱ::

፶. ወካዕበ ይቤ ኢትፍርሁ እም
እለ ይቀትሉ ሥጋክሙ፤ ወለነፍስክ
ሙሰ ኢይክሉ ቀቲሎታ ፍርሁሰ
ዘይክል ነፍሰ ወሥጋ አኅጕሎ
በውስተ ገሃነም::[፫]

፶፩. እስመ ዘተምህረ ኪነ ርቱዕ
ውእቱኒ ይምህር ካልአነ::

፶፪. ወእመሰ ኢመሀረ ካልአነ ኢኮነ
ፍጹመ ከመ መምህሩ::

፫. ማቴ. ፲፥፳፰–፴፱

፵፭. ስለዚህም ጌታችን መለሰ፤
እንዲህም አለ፤ በሰው ፊት የሚክ
ደኝን እኔም በሰማያዊው አባቴ
ፊት እክደዋለሁ::

፵፮. ሁለተኛም ከኔ ይልቅ እናትና
አባቱን የሚወድ ለእኔ ሊሆን
አይገባውም፤ ከእኔም ይልቅ ወንድ
ልጁንና ሴት ልጁን የሚወድ ለእኔ
ሊሆን አይገባውም ብሎ አዘዘ::

፵፯. የሞቱን መስቀል የማይዝ በኋ
ላዬም የማይከተለኝ ለእኔ ሊሆን
አይገባውም::

፵፰. ነፍሱን የሚያገኝ ያጠፋታል፤
ነፍሱንም ስለ እኔ የሚያጠፋ
ያገኛታል::

፵፱. ሰው ዓለሙን ሁሉ ቢገዛ
ነፍሱን ከጐዳ ምን ይጠቅመዋል?
ለነፍሱስ ቤዛ ምን በሰጠ ነበር?
አለ::

፶. ሁለተኛም ሥጋችሁን ከሚገ
ድሉ የተነሣ አትፍሩ፤ ነፍሳ
ችሁን መግደል አይችሉምና፤ ነፍስ
ንና ሥጋን በገሃነም ሊያጠፋ
የሚችለውን ግን ፍሩ::

፶፩. ጥበብን የተማረ እርሱም ሌሎ
ችን ያስተምር ዘንድ ይገባልና ::

፶፪. ሌሎችን ካላስተማረ ግን እንደ
መምህሩ ፍጹም አይሆንምና::



፶፫. ለነሰ ኢየሱስ ክርስቶስ መድ
ኀኒነ ወመምህርነ እፎኬ ናፈቅር
ትምህርተ ወተግሣጸ እስመ ጸልአ
እግዚእነ ትዕቢተ ወትዝኅርተ ወት
ፍሥሕተ ወብዕለ ወትዕግልተ
ወበቀለ::

፶፬. ወዓዲ መነነ እኀተ ወእመ
በእንተ ፍቅረ አቡሁ ወፍቅረ
ሰብእ::

፶፭. ወካዕበ ተዐገሠ ሕማመ
ወመቅሠፍተ ወጽዕለተ ወፅርፈተ
ወሥላቀ::

፶፮. ወፈድፋደሰ ተወክፈ ቅንዋተ
በዲበ መስቀል ከመ ያድኅኖሙ
ለኵሎሙ እለ አምኑ ቦቱ

፶፯. ወእመሰ ተዐገሠ ውእቱ ዘንተ
ኵሎ ወኢኀፈረ ተሰቅሎ በዲበ
መስቀል ወተዐገሠ ሕማማተ
ሞት እፎኬ ኢንትዔገሥ ንሕነ
ሕማማተ መድኀኒነ::
፶፰. ወእመሰ ሐመ በፈቃዱ
በእንቲአነ ወአኮ ንሕነ በእንቲአሁ
አላ ዳዕሙ ንሴፎ ምሕረቶ::

፶፱. ወውእቱሰ አልቦ ዘይፈቅድ
ይንሣእ በኀቤነ ዘእንበለ ዳዕሙ
አሚነ በርትዕት ሃይማኖት::

፷. ወበእንተዝ ንመንን አበዊነ
ወአዝማዲነ ወፍቁራኒነ ወአንስ
ትያነ ወደቂቀነ ወኵሎ ንዋዮ ለዝ
ቱ ዓለም::

፶፫. ለኛ ግን መድኀኒታችንና መም
ህራችን ኢየሱስ ክርስቶስ ነው፤ እኛ
ትምህርትንና ምክርን እንዴት አን
ውድድ? ጌታችን ትዕቢትንና መታ
ጀርን፤ የዚህን ዓለም ደስታ ብልጽግና
ንና ቅሚያን፤ በቀልንም ጠልቷልና::

፶፬. ዳግመኛም ስለ አባቱ ፍቅርና
ስለ ሰው ፍቅር እኅትንና እናትን
ንቋልና::

፶፭. ሁለተኛም መከራንና መገረፍን፤
መሽሟጠጥንና መሰደብን፤ ስላቅንም
ታገሠ::

፶፮. ይልቁንም ያመኑበትን ሁሉ
ያድናቸው ዘንድ በመስቀል ላይ
ችንካሮችን ተቀበለ::

፶፯. እርሱ ይኸን ሁሉ ታግሦ በመ
ስቀል ላይ መሰቀልን ካላፈረ የሞት
መከራዎችን ከታገሠ፤ እኛም የመድ
ኃኒታችንን መከራዎች እንደምን
አንታገሥ?
፶፰. እርሱ ስለ እኛ በፈቃዱ መከራን
ከተቀበለ እኛ ስለ እርሱ አይደለም
ምሕረቱን ተስፋ እናደርጋለን እንጂ::

፶፱. እርሱ በቀናች ሃይማኖት ማመ
ንን ነው እንጂ፤ ከዚህ በቀር ከኛ
ዘንድ ሊቀበል የሚፈልገው የለም::

፷. ስለዚህ ነገር አባቶቻችንንና
ዘመዶቻችንን፤ ወዳጆቻችንንና ሚስ
ቶቻችንን፤ ልጆቻችንንና የዚህን
ዓለም ገንዘብ ሁሉ እንናቅ::

፳፩. ወእመሰ አፍቀርነ ኢንገብር ዘንተ ትእዛዘ::

፳፪. ወባሕቱ ንትዓቀብ ከመ ኢንባዕ ውስተ መንሱት::

፳፫. ወእምከመ ተጸዋዕነ ውስተ ስምዕ ንጽናዕ በአሚን በክቡር ስሙ ለመድኀኒነ ንትፌሣሕ::

፳፬. ወንትዓገሥ ሶበ ይሰድዱነ ከመ ንረስ ሕይወተ ዘለዓለም::

፳፭. ኢናፍቅር እንከ ክብረ ወተወድሶ ከመ ሕዝበ አይሁድ እለ ያነክሩ መንክራቲሁ ለክርስቶስ ወኢየአምኑ ቦቱ እስመ ይፈርህዎሙ ለሊቃነ ካህናት::

፳፮. አላ ዳዕሙ አብደሩ ተወድሶ በኀበ ሰብእ ወአኮ በኀበ እግዚአብሔር::

፳፯. ወንሕነሰ አመነ በርትዕት ሃይማኖት ከመ ናለብዎሙ ለሐዲሳን እለ ነሥኡ ጥምቀተ ወናጽንዕ አልባቢሆሙ ለንዑሰ ክርስቲያን ::

፳፰. ወእመሰ ዐቀብነ በአልባቢነ ሃይማኖተ ወኢያግህድነ ለሰብእ በፍርሃተ ኵነኔ ወምንዳቤ ንከውን ውፁኣነ እምሕይወት ወዓዲ ዕቅፍተ ለካልኣን ወመሥገርተ ለብዙኃን::

፳፩. ይኸን ብንወድ ግን ይህን ትእዛዝ አንሠራም::

፳፪. ነገር ግን ወደጥፋት እንዳንገባ እንጠበቅ::

፳፫. ወደ ሰማዕትነት ብንጠራ በሃይማኖት ጸንተን በመድኃኒታችን በከበረ ስሙ ደስ ይበለን::

፳፬. የዘለዓለም ሕይወትንም እንወርስ ዘንድ በአሳደዱን ጊዜ እንታገሥ::

፳፭. የክርስቶስን ተአምራቱን እያደነቁ እንደማያምኑበት እንደ አይሁድ ሕዝብ ክብርንና ውዳሴን አንውደድ፤ ሊቃነ ካህናቱን ይፈሩዋቸው ነበርና::

፳፮.. ነገር ግን በእግዚአብሔር ዘንድ ያይደለ በሰው ዘንድ ውዳሴ ከንቱን ይወዱ ነበር::

፳፯. እኛ ግን ጥምቀቱን የተቀበሉትን አዲስ አማኞች እናለብማቸውና የንዑስ ክርስቲያንንም ልቡናቸውን እናጸና ዘንድ በቀናች ሃይማኖት አምነናል::

፳፰. በልቡናችን ሃይማኖትን ብንጠብቅም ፍርድንና መከራን በመፍራት ለሰው ባንገልጥ ግን ከሕይወት የወጣን እንሆናለን፤ ዳግመኛም ለሌሎች እንቅፋት ለብዙዎችም ወጥመድ እንሆናለን::



፳፱. ወእመሰ ገበርነ ዘንተ ንትፈደይ ምክዕቢተ ኵነኔ::

፴. ንትዓቀብ እንከ ከመ ኢንረድ ውስተ ምንዳቤ ወንጸሊ ከመ ኢንባእ ውስተ መንሱት እስመ መንፈስ ይፈቅድ ወሥጋ ይደክም::[፮]

፴፩. ንለቡ እንከ ከመ ኢንድኀፅ እምዛቲ ርትዕት ሃይማኖት እንበይነ ፍርሃቶሙ ለዕልዋን ወመናፍቃን እስመ ኀዳጥ ውእቱ ዓመታቲነ::

፴፪. ወእመሰ ቦ ዘይቀብፅ ተስፋ በኀበ ኢየሱስ ክርስቶስ ወልደ እግዚአብሔር ኵሎ አሚረ ይትመነደብ በሕማም እንተ አልባቲ ፈውስ ወበሕምዝ እንተ ታጸብስ አባለ ወትቀጠቅጥ አዕፅምተ ወእምዝ የኀጕል እም ሕይወት ዘለዓለም ወይትኴነን በውስተ ገሃነም በብካይ ወሐቅየ ስነን::

፴፫. ወዘሰ ሐመ በእንተ እግዚእነ ወኮነ ሰማዕተ ይትፌሣሕ በእግዚአብሔር እስመ ኀረየ ሎቱ አክሊለ መንግሥት ወኮነ ፍጹመ ፀአተ እምዝ ዓለም በርትዕት ሃይማኖት::

፴፬. ወእመሰ ሐመ ንዑሰ ክርስቲያን ወተዓገሠ ምንዳቤ ወሞተ በእንተ ስመ ክርስቶስ ይከውኖ ሕማማቲሁ ህየንተ ጥምቀት ወይረክብ ተስፋ ሠናየ ወሕይወተ ዘለዓለም::

፮. ማቴ. ፳፮፥፵፩

፳፱. ይህነን ብናደርግ ግን እጽፍ ድርብ ቅጣትን እንቀበላለን::

፴. እንግዲህ ወደ መከራ እንዳንወርድ እንጠበቅ ወደ ፈተናም እንዳንገባ እንጸልይ፤ መንፈስ ይፈቅዳል ሥጋ ግን ይደክማልና::

፴፩. እንግዲህ ዐላውያንንና መናፍቃንን በመፍራት ከዚህች የቀናች ሃይማኖት እንዳንሰነካከል እናስተውል ዘመናችን ጥቂት ነውና::

፴፪. በእግዚአብሔር ልጅ በኢየሱስ ክርስቶስ ዘንድ ተስፋን የሚቆርጥ ቢኖር ፈውስ በሌላት ሕማም ሰውነትን በምታደርቅና በምትቀጠቅጥ መርዝ ዘወትር ይጨነቃል፤ ከዚህም በኋላ የዘለዓለም ሕይወትን ያጣል፤ ልቅሶና ጥርስ ማፋጨት ባለበት በገሀነም ይፈረድበታል::

፴፫. ስለ ጌታችን መከራን የተቀበለና ሰማዕት የሆነ ግን በእግዚአብሔር ዘንድ ደስ ይለዋል የመንግሥት አክሊልን መርጦለታልና ከዚህ ዓለም ፈጽሞ መለየቱም በቀናች ሃይማኖት ሁኗልና::

፴፬. ንዑሰ ክርስቲያን ቢታመም፣ መከራንም ቢታገሥ፣ ስለ ክርስቶስም ስም ቢሞት መከራው ስለ ጥምቀት ይሆነዋል፤ መልካም ተስፋንና የዘለዓለም ሕይወትንም ያገኛል::

፳፭. ወባዕዳንሂ እለ ተጋደሉ ሠናየ ገድለ ወሞቱ በእንተ ስመ ክርስቶስ በርትዕት ሃይማኖት ይትፌሥሑ ወይትሐሠዩ እስመ ዐቀቡ ተግሣጸ መምህሮሙ::

፳፮. እስመ ውእቱ ይቤ ኩኑ ድልዋነ ከመ መምህርክሙ::

፳፯. ወእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ሐመ በእንቲአነ ወተዐገሠ ጽርፈተ ወስላቀ ወተወክፈ ምራቀ ርኩሳነ ጽዕለተ ወፅርፈተ ወዝብጠተ::

፳፰. ወእምድኅረ ቀሠፍዎ ወቀነውዎ በዲበ መስቀል ወአስተይዎ ብሒአ ዘምስለ ሐሞት ወፈጺሞ ዘጽሑፍ ይቤሎ ለእግዚአብሔር አባ ናሁ ውስተ እዴከ አመሐፅን ነፍስየ::[፩]

፳፱. ወዘሰ ይፈቅድ ይኩን ረድኦ ይትዓገሥ ሕማመ ወምንዳቤ ወይትወከፍ መቅሠፍተ በጥቡዕ ልብ ወፍቅር::

፴. ወእመኒ ተወድየ ውስተ እሳት አልቦ ዘይለክፎ በከመ ድኅኑ ፫ቱ ደቂቅ እምዕቶነ እሳት::

፴፩. ወኵሉ ዘሐመ በእንቲአሁ ይነሥእ ዕሤተ እስመ አምነ በ፩ እግዚአብሔር አብ ወኢየሱስ ክርስቶስ ዐቢይ ሊቀ ካህናት መምህርነ ወመገሥጸ ነፍሳቲነ ወወሀቤ ሕይወትነ ሎቱ ስብሐት ለዓለመ ዓለም አሜን::

፩. ሉቃ. ፳፫ ፥ ፵፮

፳፭. በጎ መጋደልን የተጋደሉ ሌሎችም ስለ ክርስቶስ ስም በቀናች ሃይማኖት የሞቱ ፈጽመው ደስ ይላቸዋል፣ የመምህራቸውን ምክር ጠብቀዋልና::

፳፮. እርሱ እንደ መምህራችሁ የበቃችሁ ሁኑ ብሏልና::

፳፯. ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ስለኛ መከራን ተቀበለ፣ ጽርፈትንና ሥላቅን ታገሠ፣ የርኩሳንንም ምራቅና ስድብን ሽሙጥንና ድብደባንም ተቀበለ::

፳፰. ከገረፉትና በመስቀል ላይ ከቸነከሩት መጻጻንም ከሐሞት ጋራ ከአጠጡት በኋላ፣ የተጻፈውን ፈጽሞ እግዚአብሔርን አባቴ እነሆ ነፍሴን በእጅህ አደራ እሰጣለሁ አለው::

፳፱. የእርሱ ደቀ መዝሙር ሊሆን የሚወድ መከራንና ጭንቅን ይታገሥ በቈራጥ ልብና በፍቅር ሁኖ ግርፋትን ይቀበል::

፴. ወደ እሳት ቢጨመርም ሠለስቱ ደቂቅ ከእቶነ እሳት እንደ ዳኑ የሚነካው የለም::

፴፩. ስለእርሱ መከራን የተቀበለ ሁሉ ዋጋውን ያገኛል፣ በአንድ በእግዚአብሔር አብ ሕይወትን በሚያድለን ሰውነታችንን በሚመክርና በሚያስተምር በደገኛው ሊቀ ካህናት በኢየሱስ ክርስቶስ አምኗልና፣ ለዘለዓለሙ በእውነት ለእርሱ ክብር ይገባል::



፴፪. ውእቱኬ እግዚአብሔር አምላክ አኃዜ ኵሉ መድኅኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ ዘያጸንዖነ ውስተ ሃይማኖተ ዚአሁ ወያነሥአነ ምስለ እለ ገብሩ ፈቃዶ ዘእንበለ ሕፀት ወኖሙ::

፴፫. ወእመኒ ተሰጠምነ ውስተ ባሕር ወበልዑ ሥጋነ አራዊት ወአዕዋፍ ኢትትኀጐል ወኢአሐቲ ሥዕርተ ርእስነ እስመ ዘበዓለም ወኵሉ ዘውስቴታ እትኀዝ ውስተ እዴሁ::

፴፬. ወበእንተዝ መሀረነ እንዘ ይብል በትዕግሥትክሙ ታጠርይዋ ለነፍስክሙ::

፴፭. እስመ ይትነሣእ በደኃሪት ዕለት ኵሉ ፍጥረተ ሰብእ ጻድቅ ወኃጥእ ::

## አንቀጽ ፳ ወ ፭

በእንተ ትንሣኤ ሙታን፣

፩. ወበእንተ ትንሣኤ ምውታን ወዕሤተ ሰማዕት ይቤሎ ገብርኤል ለዳንኤል ብዙኃን እለ ኖሙ ይትነሥኡ እምነ ፀበል::

፪. ወቦ እለ ይትነሥኡ ውስተ ሕይወት ዘለዓለም ወቦ እለ ይትነሥኡ በሀፍረት ወበኃሣር::[፩]

፫. ጻድቃንሰ ይበርሁ ከመ ፀሐይ ወከመ ከዋክብት ብሩሃን::

፩. ዳን. ፲፪ ፥ ፪–፫

፴፪. ይኸውም ሳያጓድሉ ፈቃዱን ሠርተው ከሞቱት ጋራ የሚያስነሣን እርሱን በማመን የሚያጸናን ሁሉን የያዘ አምላካችንና መድኃኒታችን እግዚአብሔር ኢየሱስ ክርስቶስ ነው::

፴፫. በባሕር ብንሰጥምም ሥጋችንንም አራዊትና አዕዋፍ ቢበሉት፣ አንዲት ስንኳ የራስ ጸጒራችን አትጠፋም በዓለምና ውስጥዋ ያለው ሁሉ በእጁ የተያዘ ነውና::

፴፬. ስለዚህም በትዕግሥታችሁ ነፍሳችሁን ገንዘብ ታደርጓታላችሁ ብሎ አስተማረን::

፴፭. በኋለኛይቱ ቀን የሰው ፍጥረት ሁሉ ጻድቁም ኃጥኡም ይነሣልና::

## ሀያ አምስተኛ አንቀጽ

ስለ ሙታን መነሣት ይናገራል፣

፩. ስለ ሙታን መነሣትና ስለ ሰማዕታት ዋጋ ገብርኤል ለዳንኤል እንዲህ አለው፣ የሞቱ ብዙ ሰዎች ከትቢያ ይነሣሉ::

፪. ለዘለዓለም ሕይወት የሚነሡ አሉ፣ ለኀፍረትና ለኃሣር የሚነሡም አሉ::

፫. ጻድቃን ግን እንደ ፀሐይና እንደ ከዋክብት ይበራሉ::

፬. ናሁ ቅዱስ ገብርኤል አቅደመ ነጊረ ወይቤ ወይበርሁ ቅዱሳን ከመ ከዋክብት ብሩሃን::

፭. ወዓዲ ስምዐ ኮነ በእንተ አሆሙ ከመ የአምርዋ ለጽድቅ ወይሌብዉ ስሞ ቅዱሰ::

፮. እስመ ኢይቤ ዘንተ በእንተ ትንሣኤ ሙታን ሰማዕት ባሕቲቶሙ፣ አላ ባሕቱ በእንተ ትንሣኤ ኵሉ ሰብእ እመሂ ጻድቃን አው ኃጥአን ይትፈደዩ ፩፩ በከመ ምግባሮሙ::

፯. እስመ ይቤሉ አይሁድ ትንሣኤ ሙታን አልቦ ናሁ አዕፅምቲነ ኮነ ሐመደ ወበልየ ሥጋነ::፬

፰. ወለእለ ይኄልዩ ዘንተ ያወሥኦሙ እንዘ ይብል ናሁ አነ እከሥት መቃብሪክሙ ወአወጽአክሙ እምኔሁ ወእሬሲ መንፈስየ ላዕሌክሙ ወተሐይዉ ይእዜ ተአምሩ ከመ አነ ውእቱ እግዚአብሔር ዘእነብር ወእገብር::

፱. ወዓዲ ይቤ ኢሳይያስ "ሙታን ይትነሥኡ ወየሐይዉ እለ ውስተ መቃብር ወይትፌሥሑ እለ ውስተ ምድር እስመ ጠል ዘእምኀቤከ ሕይወቶሙ ውእቱ::" ፭

፬. ፩ኛ ተሰሎ. ፬፥ ፲፫-፲፬

፭. ኢሳ. ፳፮ ፥ ፲፰

፬. እነሆ ቅዱስ ገብርኤል አስቀድሞ ቅዱሳን እንደሚያበሩ ከዋክብት ይበራሉ ብሎ ተናገረ::

፭. ዳግመኛም ጽድቅን እንደሚያውቋትና ቅዱስ ስሙንም እንደሚያስተውሉ ስለ እነርሱ መሰከረ::

፮. ስለ ሞቱ ሰማዕታት ትንሣኤ ብቻ ይህን አላለምና፣ ስለ ሁሉም ሰው ትንሣኤ ነው እንጂ፣ ጻድቃንም ቢሆኑ ኃጥአንም ቢሆኑ እያንዳንዳቸው እንደ ሥራቸው ይቀበላሉ::

፯. አይሁድ የሙታን ትንሣኤ የለም፣ እነሆ አጥንታችንም አመድ ይሆናል ሥጋችንም ይፈርሳል ይላሉና::

፰. ይህን ለሚያስቡት እንዲህ ብሎ ይመልስላቸዋል፣ እነሆ እኔ መቃብራችሁን እከፍታለሁ፣ ከእርሱም አወጣችኋለሁ፣ መንፈሴንም አሳድርባችኋለሁ፣ ትነሣላችሁም፣ ያን ጊዜም የምኖር የማደርግም እኔ እግዚአብሔር እንደሆንሁ አሁን ታውቃላችሁ::

፱. ዳግመኛም ኢሳይያስ ሙታን ይነሣሉ፣ በመቃብር ያሉትም ይድናሉ፣ በምድር ያሉትም ደስ ይላቸዋል፣ ካንተ የተገኘ ጠል ሕይወታቸው ነውና አለ ::



፲. ብዙኀ ጊዜ ነገረነ በእንተ ትንሣኤ ሙታን ወንብረተ ውስተ ሕይወት ዘለዓለም እንተ ምልዕተ ጸጋ ወጽድቅ ዘአስተዳለወ ለእለ ያፈቅርዎ::

፲፩. ወኵነኔ ዕልዋንሰ ወድቀቶሙ ኀፍረት ወኀሣር ይረክቦሙ እሳት እንተ ኢይጠፍዕ ለዓለም ወዕፄ ዘኢይነውም::

፲፪. ወባሕቱ እግዚአብሔርሰ ኢይፈቅድ ሞቶ ለኃጥእ አላ ዳዕሙ ሚጠቶ ወሕይወቶ::፮

፲፫. ወናሁ ነገረነ ከመ ሄኖክ ወኤልያስ ኢጥዕምዎ ለሞት፣ ወአጠየቀነ ከመ ይትነሥኡ ሙታን በጊዜሁ፣ አንሥአ ኤልያስ ወልደ መበለት፣ ወኤልሳዕኒ አንሥአ ወልዳ ለሱናማዊት፣ ናሁ ለበውነ ከመ ሞቶሙ ለጻድቃን ኢኮነ ኵነኔ እለ ተወክፍዎ ቅዱሳን በፍሥሓ::

፲፬. ወከማሁ ኢየሱስ ክርስቶስ እግዚኦሙ ለሐዋርያት ወሕይወቶሙ ለመሃይምናን ያነሥኦሙ ለሙታን::

፲፭. ወከማሁ ንሕነኒ ንጻሙ በዝ ዓለም ወእምድኅረ ኀዳጥ ንፈልስ ውስተ ዕረፍት::

፮. ሉቃ. ፲፰ ፥ ፲፬

፲. ስለ ትንሣኤ ሙታን ብዙ ጊዜ ነገረን፣ ለሚወዳቸው ሰዎች በአዘጋጃት ጸጋንና ጽድቅን በተመላች በዘለዓለም ሕይወት ስለ መኖር ብዙ ጊዜ ነገረን ::

፲፩. የከሀድያን መከራ ግን ኃፍረት ኃሣር የሚሆን መውደቃቸውም ለዘለዓለሙ የማይጠፋ እሳት፣ የማያንቀላፋ ትል ያገኛቸዋል::

፲፪. ነገር ግን እግዚአብሔር የኃጥእን ሞት አይፈቅድም፣ መመለሱንና መዳኑን ነው እንጂ ::

፲፫. እነሆ ሄኖክና ኤልያስ ሞትን እንዳልቀመሱት ነገረን፣ ሙታንም በጊዜው እንደሚነሡ አስረዳን፣ ኤልያስ የመበለቲቱን ልጅ ከሞት አስነሥቷል፤ ኤልሳዕም የሱናማዊቲቱን ልጅ አስነስቷል፣ እነሆ የጻድቃን ሞታቸው ቅዱሳን በደስታ የተቀበሉት ኵነኔ እንዳይደለ አስተዋልን::

፲፬. እንደዚሁም የሐዋርያት ጌታቸው፣ የምእመናን ሕይወታቸው ኢየሱስ ክርስቶስ ሙታንን ያነሣቸዋል::

፲፭. እንደዚሁም እኛ በዚህ ዓለም እንደክማለን፣ ከጥቂት ዘመን በኋላም ወደ ዕረፍት እንሄዳለን::

፲፮. ወትትሔደስ ፍጥረቱ ለአዳም ወንትነሣእ ምስሌሁ ውስተ ሕይወት ዘለዓለም እስመ ይቤ ይሰምዑ ቃሎ ምውታን ወኵሎሙ እለ ይሰምዑ የሐይዉ::[5]

፲፯. ወበእንተዝ ነአምን ከመ ትንሣኤ ሙታን ዳግመ በምጽአቱ ለክርስቶስ::

፲፰. ወዓዲ ውእቱ ዘአንሥኦ ለአልዓዛር እመቃብር፣ በራብዕት ዕለት ወለወለተ ኢያኢሮስ፣ ወለወልደ መበለት አንሥኦሙ እሙታን[6] ወለሊሁኒ ተንሥአ እሙታን በሣልስት ዕለት በሥምረተ አቡሁ ወኮነ ቃለ ሕይወት::

፲፱. ወዓዲ ውእቱ ዘአውፅኦ ለዮናስ እምከርሠ አንበሪ በሣልስት ዕለት እንዘ ሕያው ውእቱ ዘእንበለ ሙስና::[7]

፳. ወለሠለስቱ ደቂቅ አድኅኖሙ እምዕቶነ እሳት በሀገረ ባቢሎን::[8]

፳፩. ወለዳንኤል እምአፈ አናብስት::[9]

፳፪. ውእቱኬ ዘቦቱ ሥልጣን ወኀይል ያንሥኦሙ ለሙታን በደኃሪት ዕለት::

፭. ዮሐ. ፭ ፥ ፳፭
፮. ሉቃ. ፯ ፥ ፲፬-፲፭
፯. ዮና. ፪ ፥ ፩-፲፩
፰. ዳን. ፫ ፥ ፺፱
፱. ዳን. ፮ ፥ ፲፯

፲፮. የአዳም ተፈጥሮ ትታደሳለች፣ ከእርሱም ጋር ለዘለዓለም ሕይወት እንነሣለን፣ ሙታን ቃሉን ይሰማሉ፣ የሚሰሙትም ሁሉ ይነሣሉ ብሎአልና::

፲፯. ስለዚህም የሙታን ትንሣኤ የክርስቶስ ዳግም መምጣት እንደ ሆነ እናምናለን::

፲፰. ዳግመኛም አልዓዛርን በአራተኛው ቀን ከመቃብር ያሥነሳው፣ የኢያኢሮስን ሴት ልጅና የመበለቲቱን ወንድ ልጅ ያስነሣቸው፣ እርሱ ነው፤ እርሱም ራሱ በሦስተኛው ቀን በአባቱ ፈቃድ ከሙታን ተለይቶ ተነሣ፣የሕይወትም ቃል ሆነ::

፲፱. ዳግመኛም ዮናስን በሕይወት ሳለ ያለጥፋት በሦስተኛው ቀን ከዓሣ አንበሪ ሆድ ያወጣው እርሱ ነው::

፳. ሦስቱ ደቂቅንም በባቢሎን ሀገር ከእቶነ እሳት አዳናቸው::

፳፩. ዳንኤልንም ከአንበሶች አፍ አዳነው::

፳፪. በኋለኛይቱ ቀን ሙታንን ያነሣቸው ዘንድ ሥልጣንና ኃይል ያለው እርሱ ነው::



፳፫. ወእመሰ ዕልዋን እለ ኢየአምኑ ቅዱሳተ መጻሕፍተ ይሣለቁ ላዕሌነ፣ ናሁ ነቢይተ ዚአሆሙ ታጌብሮሙ ከመ ይእመኑ ዘይብሎሙ ከመዝ በቃል ዘይረውጽ ፍጡነ፣ እምከመ ገብአ ኵሉ ነገር ውስተ መሬት ወሐመድ ወእግዚአብሔር ሕያው ዘአንደደ እሳተ ወአጥፍአ ያነሥኦሙ ለአዕፅምት ወሐመድ ዳግመ ወያቀውሞሙ ለሰብእ ምውታን ከመ ቀዳሚ ::

፳፬. አሜሃ ይከውን ኵነኔ ሶበ ይገብር እግዚአብሔር ፍትሐ ::

፳፭. ወይኴንን እግዚአብሔር ኵሎ ዓለመ::

፳፮. ወእለሰ ይገብሩ ኀጢአተ ይወርዱ ውስተ ማዕምቅተ ምድር::

፳፯. ወእለሰ የአቅቡ ትእዛዞ የሐይዉ ሕይወተ ዘለዓለም ሶበ ይሁቦሙ እግዚአብሔር መንፈሰ ሕይወት ወእለ ይድኅኑ ይትረአዩ በበይናቲሆሙ::

፳፰. ወእመሰ ቦ እለ ኢየአምኑ ቦቱ ትንሣኤ፣ ያስሕቱ ካልአ ፍጥረተ ናሁ ያሌብዎሙ ለዕልዋን ለእለ ይብሉ አልቦ ትንሣኤ ሙታን ዖፍ ዘ፩ ፍጥረቱ ዘስሙ ፊንክስ::

፳፫. ቅዱሳት መጻሕፍትን የማያምኑ ከሐድያን ግን በኛ ቢሳለቁብን እነሆ የነሱ ነቢይት ፈጥኖ በሚሄድ ቃል የሚናገራቸውን ያምኑ ዘንድ ታስገድዳቸዋለች፣ ሁሉም ነገር ወደ አፈርና ትቢያ ከተመለሰ በኋላ እሳትን ያቀጣጠለና ያጠፋ ሕያው እግዚአብሔር አጥንቶችንና ትቢያውን ያስነሣቸዋል፣ የሞቱትንም ሰዎች እንደ ቀድሞው ያቆማቸዋል::

፳፬. ያን ጊዜ እግዚአብሔር ፍርድ በሚያደርግበት ጊዜ የቅጣት ፍርድ ይሆናል::

፳፭. ያን ጊዜ እግዚአብሔርም በዓለሙ ሁሉ የቅጣት ፍርድን ይፈርዳል::

፳፮. ኃጢአትንም የሚሠሩ ወደ ጥልቅ ምድር ይወርዳሉ::

፳፯. ትእዛዙን የሚጠብቁ ግን እግዚአብሔር የሕይወት መንፈስን በሰጣቸው ጊዜ ለዘለዓለም ይነሣሉ፣ የሚድኑትም እርስ በእርሳቸው ይተያያሉ::

፳፰. ትንሣኤ ሙታንን የማያምኑ ሰዎች ቢኖሩ ግን፣ ሌሎቹን ሰዎች እንዳያስቱ ትንሣኤ ሙታን የለም የሚሉ ወንጀለኞችን ስሙ ፊንክስ የሚባል ተፈጥሮው አንድ የሚሆን ዖፍ ያስረዳቸዋል::

፳፱. ወይብሉ በእንተ ውእቱ ዖፍ የሐዩ ፭ተ ፻ተ ዓመተ፣ ወእምዝ ይወርድ ውስተ ግብጽ ወያመጽእ ምስሌሁ ቀናንሞስ ወሰሊሆተ ውሑደ፣ ወይነብር ውስተ ሥዕለ ጣዖት ዘስሙ ኤዎን ወይሬኢ ውስተ ምሥራቅ ወይሰግድ ለፀሐይ::

፴. ወእምዝ ይውዒ፣ ወይከውን ሐመደ፣ ወይወፅእ እምውእቱ ሐመድ ፩ ዕፄ ንኡስ፣ ወያመውቆ ፀሐይ ለውእቱ ዕፄ ወይከውን ንኡሰ ዖፈ ፈንክስ ወልሂቆ ይገብእ ውስተ ብሔረ ዓረብ::

፴፩. ወእመሰ የአምሩ እሙንቱ ተሐድሶቶ ለውእቱ ዖፍ እፎኬ ይትገዓዙነ በእንተ ዘንብል በእንተ ትንሣኤ ሙታን ወነአምን::

፴፪. ዘፈጠሮ ለሰብእ እምኀበ ኢሀሎ ኢይክልኑ አንሥኦቶሙ ለምውታን በዐቢይ ኀይሉ::

፴፫. ወበእንተዝ ይደልወነ ንትዓገሥ ሕማመ ወምንዳቤ ዘዘዚአሁ ዘይመጽእ ላዕሌነ::

፴፬. ወእመሰ ኢነአምኖ ትንሣኤ ሙታን ይከውን ሕማምነ ወምንዳቤነ ከንቶ::

፴፭. ወእመሰ አመነ በዘይቤ ውእቱ ሙሴ በቀዳሚ ገብረ እግዚአብሔር ሰማየ ወምድረ::

፳፱. ስለዚያም ዖፍ እንዲህ ይላሉ፣ አምስት መቶ ዓመት ይኖራል፣ ከዚያም በኋላ ወደ ግብጽ ይወርዳል፣ ቀናንሞስ፣ ሰሊሆትና ዑድ፣ የሚባለውን ሽቱ ከርሱ ጋራ ያመጣል፤ ስሙ ኤዎን በሚባል ጣዖት ፊት ተቀምጦ ወደ ምሥራቅ ይመለከታል፣ ለፀሐይም ይሰግዳል::

፴. ከዚህም በኋላ ተቃጥሎ አመድ ይሆናል፣ ከዚያም ከአመዱ አንድ ትንሽ ትል ይወጣል፣ ያነንም ትል ፀሐይ ያሞቀዋል፣ ፈንክስ የሚባለውን ታናሽ ዖፍንም ይሆናል ፣ ባደገም ጊዜ ወደ ዐረብ አገር ይመለሳል::

፴፩. እነርሱ የዚያን የዖፍ መታደስ የሚያውቁ ከሆነ ስለ ትንሣኤ ሙታን ስለምንናገርና ስለ ምናምን እንደምን ይከራከሩናል?

፴፪. ሰውን ካለመኖር የፈጠረ እግዚአብሔር በፍጹም ከሃሊነቱ ሙታንን ማስነሣት አይችልምን::

፴፫. ስለዚህም በኛ ላይ የሚመጣውን ልዩ ልዩ መከራና ችግር እንታገሥ ዘንድ ይገባናል::

፴፬. ትንሣኤ ሙታንን ባናምን ግን መከራችንና መቸገራችን ከንቱ ይሆናል::

፴፭. እርሱም ሙሴ በመጀመሪያ እግዚአብሔር ሰማይና ምድርን ፈጠረ በአለው ...



፴፮. ወውእቱሰ አልቦ ዘይጽሕቅ ወኢምንተኒ አእሚሮ ከመ ኵሉ በቃሉ ይትገበር ሠምረ ይኩን፣ ሰማይ ወምድር ወማይ ወብርሃን ወጽልመት ወሌሊት ፀዳል ወከዋክብት፣ ወአዕዋፍ ወአንበሪ ወእንስሳ ወአራዊት ወዕፀው ወሐመልማል::

፴፯. ከማሁ ያነሥኦሙ ለኵሎሙ በፈቃዱ፣ ወኢይፈቅድ ካልዓ ረዳኤ::

፴፰. ዝውእቱ ዘይክል በኀይሉ የሐድስ ዓለመ ዳግመ ወያንሥኦሙ ለሙታን::

፴፱. ወባሕቱ ሰብእሰ ኢቀደመ ተፈጥሮ አላ ዳዕሙ ፈጠሮ እምፅቱ ጠባይዓት ወወሀቦ ነፍሰ::[፲]

፵. ወከማሁ ይሁብ ለዛቲ ነፍስተ ሥጋ ዘትማስን ::

፵፩. እስመ ትንሣኤሰ ለእለ ኖሙ ወአኮ ለእለ ኢተፈጥሩ እስመ ውእቱ ፈጠረ እምኀበ አልቦ ሥጋ ወረሰየ ውስቴቱ ብዙኀ ትእምርተ::

፵፪. ወዓዲ ውእቱ ያድኅኖሙ ወያነሥኦሙ ለእለ ኖሙ ከመ ውእቱ ፈጠረ ሥጋ ዘዘርዐ በውስተ ከርሥ::

፵፫. በከመ ይቤ ኤርምያስ ነቢይ ዘእንበለ እፍጥርከ በከርሠ እምከ አእመርኩከ::[፲፩]

፴፮. እርሱ ምንም የሚሻው የለም፣ ሁሉ በቃሉ እንዲደረግ አውቆ ሰማይና ምድር፣ ውሃም ብርሃንና ጨለማ፣ ሌሊትና ፀዳል ከዋክብትም፣ አዕዋፍና አንበሪ፣ እንስሳና አራዊትም፣ ዕፀዋትና ልምላሜም ይሆን ዘንድ ወደደ::

፴፯. እንደዚሁ በፈቃዱ ሁሉን ያነሣቸዋል፣ ሌላ ረዳት አይሻም::

፴፰. በከሃሊነቱ ዓለምን ዳግመኛ ያድስ ዘንድ ሙታንንም ያነሣ ዘንድ የሚቻለው ይህ ነው::

፴፱. ነገር ግን ሰው አስቀድሞ አልተፈጠረም፣ ከአራቱ ባሕርያት ፈጥሮ ነፍስን አሳደረበት እንጂ::

፵. እንደዚሁም ለዚች ለምትፈርስ ደመ ነፍስ ይሰጣል ::

፵፩. ትንሣኤስ ለሞቱ ነውና፣ ላልተፈጠሩም አይደለም፣ እርሱ ሥጋን እምኀበ አልቦ ፈጥሮአልና፣ በውስጡም ብዙ ምልክትን አድርጓልና::

፵፪. ዳግመኛም እርሱ በዘር የተገኘ ሥጋን በማኅፀን እንደ ፈጠረ፣ እርሱ ያድናቸዋል፣ የሞቱትንም ያስነሣቸዋል::

፵፫. ለነቢዩ ኤርምያስ በናትህ ማኅፀን ሳልፈጥርህ አወቅሁህ ብሎ እንደ ተናገረ::

፲፩. ኤር. ፩፥ ፬ - ፩

፵፬. ወካዕበ ይቤ አነ እግዚአብሔር ፈጠርኩ ሰማየ ወሣረርክዋ ለምድር ወእፈጥር ነፍሰ ላዕለ ሰብእ::

፵፭. በከመ ይቤ መጽሐፍ በእንተዝ ይቤ እግዚአብሔር ንግበር ሰብአ በአርአያነ ወበአምሳሊነ::

፵፮. ወእምዝ ፈጠሮሙ እግዚአብሔር ተባዕተ ወአንስተ::[፲፪]

፵፯. ወዓዲ ይቤ ቅዱስ ኢዮብ መዋኢ ዘበእንቲአሁ ይቤ በመጽሐፍ ከመ ውእቱ ይትነሣእ ምስለ እለ ያነሥኦሙ እግዚአብሔር::

፵፰. ከመዝ ይቤ ከመ ሀሊብ ሐለብከኒ ወአርጋዕከኒ ከመ ግብነት ወአልበስከኒ ሥጋ ወማዕሰ ወአሠርከኒ አዕፅምትየኒ በአሥራው ወወሀብከኒ ሣህለ ወምሕረተ::[፲፫]

፵፱. ወሐውጾትከ ዐቀበኒ መንፈስየ ዝንቱ በኅቤከ ሀሎ አአምር ከመ ኵሎ ትክል ወአልቦ ዘይስአነከ ወኢምንትኒ::

፶. ወካዕበ ይቤ ዳዊት መፍቀሬ እግዚአብሔር "እደዊከ ገብራኒ ወለሐኳኒ አለብወኒ ወእትመሀር ትእዛዘከ"::[፲፬]

፵፬. ዳግመኛም እኔ እግዚአብሔር ሰማይን ፈጠርኩ፣ ምድርንም መሠረትኋት፣ ነፍስንም በሰው ላይ እፈጥራለሁ ::

፵፭. ስለዚህ ነገር መጽሐፍ እንዳለ "እግዚአብሔር በመልካችን በምሳሌያችን ሰውን እንፍጠር አለ"::

፵፮. ከዚህም በኋላ እግዚአብሔር ወንድና ሴት አድርጎ ፈጠራቸው::

፵፯. ዳመኛም ድል የነሣ ቅዱስ ኢዮብ ስለ እርሱ በመጽሐፍ እግዚአብሔር ከሚያስነሣቸው ጋር እርሱም እንደሚነሣ እንዲህ አለ ::

፵፰. እንደ ወተት አልበኸኝ እንደ እርጎም አርግተህ ሥጋንና ቁርበትን አለበስኸኝ፣ አጥንቶቼንም በሥሮች (በጅማቶች) አሠርከኝ፣ ይቅርታንና ምሕረትን ሰጠኸኝ::

፵፱. መጐብኘትህም ጠበቀኝ፣ ይህ ሰውነቴም በአንተ ዘንድ አለ፣ ሁሉን እንደምትችል የሚሳንህም እንደሌለ አውቃለሁ::

፶. ሁለተኛም የእግዚአብሔር ወዳጅ ዳዊት እንዲህ አለ፣ እጆችህ ሠሩኝ ፈጠሩኝም፣ ትእዛዝህን እማር ዘንድ እንዳስተውል አድርገኝ ::

፲፪. ዘፍ. ፩፥፳፮–፳፰
፲፫. ኢዮ. ፲ ፥ ፲
፲፬. መዝ. ፻፲፰፥፸፫



፶፩. ወዓዲ ይቤ አንተ ፈጠርከኒ ወወደይከ እዴከ ላዕሌየ መንክር ግብርከ ወነፍስየ ትጤይቆ ጥቀ ወኢይትኀባዕ እምኔከ አዕፅምትየ ዘገበርኮ በኅቡእ ወኢአካልየ በመትሐተ ምድር ወዘሂ ገበርኩ ርእያ አዕይንቲከ ወኵሉ ይጸሐፍ ውስተ መጽሐፍከ ::[፲፭]

፶፪. ወኢሳይያስኒ ይቤ ንሕነሰ መሬት ወአንተ ፈጠርከነ ::

፶፫. ወእመሰ ሰብእ ፍጥረተ እግዚአብሔር ዘኮነ በክርስቶስ ይትነሥኡ ምስለ ክርስቶስ ወይነሥኡ ክብረ ወአክሊለ ሕይወት እለ ይገብሩ ፈቃዶ ኮማሁ ዕልዋን ወመናፍቃን እለ ኢይትዌከፉ ጥምቀተ ወኢየአምኑ ትንሣኤ ይትኴነኑ በመቅሠፍት ዘለዓለም::

፶፬. ወእለሰ ሠናየ ገብሩ ይበርሁ ከመ ከዋክብተ ብርሃን፣ እስመ ይቤ ዳዊት ምእመን እግዚአብሔር በኵሉ ቃሉ ወጻድቅ በኵሉ ምግባሩ::[፲፮]

፶፭. ፈጠረ ሎቱ ሥጋ እምድንግል ዘውእቱ ፈጣሬ ኵሉ ፍጥረት ውእቱ ባሕቲቱ ዘተንሥአ እሙታን ወዓዲ ውእቱ መንሥኤሆሙ ለኵሎሙ ሙታን ::

፶፩. ዳግመኛም አለ ፣ አንተ ፈጠርከኝ፣ እጅህንም በእኔ ላይ ጣልህ፣ ሥራህ ድንቅ ነው፣ ነፍሴም ፈጽማ ትረዳዋለች፣ አጥንቶቼም በሥውር የሠራኸው ከአንተ አይሠወርም፤ አካሌም ከምድር በታች የሠራሁትንም አይኖችህ አዩ ፤ ሁሉም በመጽሐፍህ ይጻፋል::

፶፪. ኢሳይያስም እኛ መሬት ነን፤ አንተ ፈጠርከን አለ ::

፶፫. በክርስቶስ የተፈጠሩ የእግዚአብሔር ፍጥረቶች ሰዎች ከክርስቶስ ጋራ ከተነሡ ፈቃዱን የሚያደርጉ ክብርንና አክሊልን የሚቀበሉ ከሆነ እንዲሁ ትንሣኤ ሙታንን የማያምኑ ጥምቀትን ያልተቀበሉ ወንጀለኞችና መናፍቃን የዘለዓለም መቅሠፍት ይፈረድባቸዋል::

፶፬. በጎ ሥራን የሠሩ ግን እንደ ብርሃን ከዋክብት ይበራሉ፣ ዳዊት እግዚአብሔር በቃሉ ሁሉ የታመነ ነው በሥራውም ሁሉ እውነተኛ ነው ብሏልና::

፶፭. ፍጥረትን ሁሉ የፈጠረ እርሱ ከድንግል ለራሱ ሥጋን ፈጠረ፤ እርሱ ብቻውን ከሙታን ተነሣ፤ ዳግመኛም ሙታንን ሁሉ የሚያስነሣቸው እርሱ ነው ::

፲፭. መዝ. ፻፴፰ ፥ ፲፭–፲፮
፲፮. [illegible]

፶፮. ዘያበቍል እምድር ኅጠተ ሥር ናይ ወያበዝኃ ፍሬሃ ወዕፀኒ እንተ ተገዝመት ይክል አብቍሎ ወአብ ዝኖ አዕፁቂሃ ወለበትረ አሮን እም ድኅረ የብሰት ረሰያ ትሥርፅ ከማሁ ይክል አንሥኦተነ ምስሌሁ::

፶፯. በስብሐት ዘዐርገ ዘአርትዐ እግረ ሐንካሳን፣ ወአሕየወ መፃጉዐ፣ ወፈወሶ ለዘየብሰ እዴሁ፣ ዘወረቀ ምድረ ወገብረ ፅቡረ ወቀብዖ አዕ ይንቲሁ ለዘዕውሩ ተወልደ ዘፈወሰ አባለ ሙሱነ፣ ኢይክልኑ አንሥ ኦተነ::

፶፰. ዘአጽገበ ነፍሰ ፶፻ ሰብእ እም ፭ቱ ኅብስተ ሰገም ወ፪ኤ ዓሣ ወአግ ኃሠ ዘተርፈ መሊያ ፲ወ፪ተ አስፈ ሬዳተ::

፶፱. ወዘረሰየ ማየ ወይነ፣ ዘፈነዎ ለጴጥሮስ ወነሥአ እምአፈ ዓሣ ወርቀ ዘይከውን ለጸባሕት፣ ውእ ቱኬ ዘያነሥኦሙ ለሙታን ::

፷. ናሁ ንሕነ ሰማዕቱ በእንተ ኵሉ ግብር ዘሰበኩ ነቢያት በእንቲአሁ ::

፷፩. ንሕነሰ አዕርክቲሁ በላዕነ ወሰ ተይነ ምስሌሁ ወርኢነ መንክራቲሁ ወአሕይዎቶ ሙታነ ወካዕበ ርኢነ ሕማሞ ወድካሞ ወሞቶ ወትን ሣኤሁ ::

፶፮. የስንዴ ቅንጣትን ከምድር የሚ ያበቅል፣ ፍሬዋንም የሚያበዛ፣ የተ ቈረጠች እንጨትንም እንድትበቅል የሚያደርግ፣ ጫፎችዋንም የሚያበዛ፣ የአሮንንም በትር ከደረቀች በኋላ እን ድትለመልም ያደረገ ፣ እንደዚሁ ከርሱ ጋራ እኛን ማስነሣት ይችላል።

፶፯. በክብር ያረገ፣ ያንካሶችን እግር ያቀና፣ መፃጉዕን ያዳነ፣ እጁ የደረቀ ውን ያዳነው፣ ከምድር ላይም እትፍ ብሎ ጭቃን አድርጎ ዕውር ሁኖ የተ ወለደውን ዓይኖቹን የቀባ፣ ጠፍቶ የነበረውን አካል ያዳነ፣ እርሱ እኛን ማስነሣት አይቻለውምን?

፶፰. በሁለት ዓሣና በአምስት የገ ብስ እንጀራ የአምስት ሽህ ሰዎችን ነፍስ አጥግቦ የተረፈውን አስራ ሁለት ቅርጫት መልቶ የአስነሣ ::

፶፱. ውሀውን የወይን ጠጅ ያደረገ፣ ጴጥሮስንም ልኮ ከዓሣ አፍ ለግብር የሚሆን ወርቅን ያስገኘ፣ ሙታንን የሚያስነሣቸው እርሱ ነው ::

፷. ስለ እርሱ ነቢያት ትንቢትን ለተ ናገሩለት ስለ ሥራው ሁሉ እነሆ ምስክሮች እኛ ነን ::

፷፩. እኛ ግን ወዳጆቹ ከእርሱ ጋራ በላን፣ ጠጣን፣ ተአምራቶቹንና ሙታ ንን ማስነሣቱን አየን፣ ሁለተኛም መከራውን ድካሙን ሞቱን ትንሣኤ ውን አየን ::



፷፪. ወሰማዕነ ቃሎ ወኮነ ፍቁ ራኒሁ ወነበርነ እስከ ፵ዓ ዕለት እምድኅረ ተንሥአ እሙታን መሀረነ ንዜኑ ስብከተ ወንጌል ቅዱስ ውስተ ኵሉ ዓለም ወአዘዘነ ናጥምቅ በስመ አብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ ዝውእቱ ጰራቅሊጦስ መንፈሰ ጽድቅ::

፷፫. ወዘንተ ምሂሮ ዐርገ ውስተ ሰማይ በሥጋ እንተ ነሥአ እምኀ ቤነ ኀበ አብ ዘፈነዎ ::

፷፬. ወእመሰ አመንክሙ ከመዝ ብፁዓን አንትሙ ::

፷፭. ወእመሰ ኢአመንክሙ ትከውኑ ርጉቃነ እምኔሁ እስመ ኢዐቀ ብክሙ ትእዛዞ::

አንቀጽ ፳ወ፮
በእንተ ሰማዕት

፩. ናሁ እብለከሙ፣ አዕብይዎሙ ወአክብርዎሙ ምክዕቢተ ለሰማ ዕት በከመ ኮኑ ክቡራነ በኀቤነ ወብፁዕ ያዕቆብ ወእስጢፋኖስ ቀዳሜ ሰማዕት::

፪. እሉ እሙንቱ ብፁዓን በኀበ እግዚአብሔር፣ ወኅሩያን ወቅዱሳን ሕዝብ ወንጹሓን እምኃጢአት ወአ ልቦሙ ቂም አላ እሙንቱ ገባርያነ ሰላም ወዓዲ ስሩሐን ለገቢረ ፈቃዱ ወለዐቂበ ትእዛዙ ::

፷፪. ቃሉንም ሰምተን ወዳጆቹ ሆንን፣ ከሙታን ተለይቶ ከተነሣ በኋላም እስከ አርባ ቀን ድረስ ልዩ የሚሆን የወንጌልን ትምህርት በዓለሙ ሁሉ እንነግር ዘንድ አስተማረን፣ በአብ በወ ልድ በመንፈስ ቅዱስ ስምም እና ጠምቅ ዘንድ አዘዘን፣ ይኸውም የእ ውነት መንፈስ ጰራቅሊጦስ ነው::

፷፫. ይኸንንም አስተምሮ ከኛ ዘንድ በነሣው ሥጋ ወደ ላከው አባቱ ወደ ሰማይ ዐረገ ::

፷፬. እንደዚህ ብታምኑ ንዑዳን ክቡራን ናችሁ::

፷፭. ባታምኑ ግን ከእርሱ የራቃ ችሁ ትሆናላችሁ ትእዛዙን አልጠበ ቃችሁምና::

ሀያ ስድስተኛ አንቀጽ
የሰማዕታትን ነገር ይናገራል::

፩. እነሆ ሰማዕታትን ከፍ ከፍ አድር ጓቸው፣ ፈጽማችሁም አክብሯቸው እላችኋለሁ፣ በኛ ዘንድም የሰማዕ ታት መጀመሪያ እስጢፋኖስና ንዑድ ክቡር ያዕቆብ ክቡራን እንደ ሆኑ::

፪. በእግዚአብሔር ዘንድ ንዑዳን ክቡራን የሆኑ የተመረጡ ከኃጢአት የነጹ፣ ቂም የሌላቸው እኒህ ናቸው፣ ሰውን ከሰው ጋራ ያስታርቃሉ፣ ዳግ መኛም ትእዛዙን ለመጠበቅ ፈቃዱ ንም ለማድረግ የደከሙ ናቸው እንጂ::

፫. ወበእንተዝ ይቤ ዳዊት ክቡር ሞቱ ለጻድቅ በቅድመ እግዚአብሔር ፡፡

፬. ወዓዲ ይቤ ሰሎሞን ዝክረ ጻድቅ ፍጹም በውዳሴ ፡፡

፭. ወካዕበ ይቤ ነቢይ ይትሌዓል ቀርኑ በክብር ፡፡

፮. ዘንተ ነገርነ ለእለ ኮኑ ስምዐ በጽድቅ በእንተ ስመ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ፡፡

፯. ናሁ ለበውነ ወጠየቅነ ከመ እለ ያከብርዎሙ ለሰማዕት ወለመሃይምናን እለ ተጋደሉ ሠናየ ገድለ ፈጸሙ ሩጸቶሙ ወሞቱ በእንተ ስመ ክርስቶስ በርትዕት ሃይማኖት ይረክቡ ዕሤተ ሠናየ ወሕይወተ ዘለዓለም፡፡

፰. ወእለሰ ኮኑ ስምዐ በጽድቅ፣ ወፈትሑ በርትዕ፣ ወአሥመርዎ ለእግዚአብሔር በሕይወቶሙ፣ እሉ እሙንቱ ይወርሱ መንግሥተ ሰማያት፡፡

### አንቀጽ ፳ወ፯

በእንተ ከመ ኢመፍትው ይባኡ ክርስቲያን ውስተ ቤተ ተውኔት ወዘፈን አላ ዳዕሙ ይሰብሑ ወይዘምሩ በቤተ ክርስቲያን ፡፡

፫. ስለዚህም ዳዊት የጻድቅ ሰው ሞቱ በእግዚአብሔር ዘንድ ክቡር ነው አለ፡፡

፬. ዳግመኛም ሰሎሞን የጻድቅ ሰው መታሰቢያ በምስጋና ፍጹም ነው አለ፡፡

፭. ሁለተኛም ነቢይ የጻድቅ ሰው ሥልጣን በክብር ከፍ ከፍ ይላል አለ፡፡

፮. ስለ ጌታችን ስለ ኢየሱስ ክርስቶስም በእውነት ምስክር ስለሆኑ ሰዎች ይኸን ነገርን ፡፡

፯. በቀናች ሃይማኖት ስለ ክርስቶስ ስም የሞቱ ሩጫቸውን የፈጸሙ በጎ መጋደልንም የተጋደሉ ምእመናንንና ሰማዕታትን የሚያከብሩ ሰዎች የዘለዓለም ሕይወትን በጎ ዋጋን እንዲያገኙ እነሆ አወቅን ተረዳን ፡፡

፰. በእውነት ምስክር የሆኑ፣ በሚገባ የፈረዱ፣ በሕይወታቸው እግዚአብሔርን ደስ ያሰኙ፣ እሊህ መንግሥተ ሰማያትን ይወርሳሉ ፡፡

### ሀያ ሰባተኛ አንቀጽ

በቤተ ክርስቲያን ይዘምሩ ያመስግኑ ዘንድ ነው እንጂ ክርስቲያኖች ወደ ዘፈን ወደ ጨዋታ ቤት ይገቡ ዘንድ እንዳይገባ ይናገራል ፡፡



፩. ናሁ ንመክረክሙ ኦ አኀው ፍቁራን ሠናየ ምክረ ትርኀቁ እም ነገረ ተውኔት ወአጽምዖ ማኅሌት ወእምሐውዘ መባልዕት ወፍግዓ ወእምኵሉ ምግባር ከንቱ ዘአልቦ ባቍዕ ፡፡

፪. ኢትግበሩ ለተድላ ፍትወተ ሥጋክሙ በዕለት እስመ ይቤ ነቢይ ተቀነዩ ለእግዚአብሔር በፍርሀት ወተሐሠዩ ሎቱ በረዓድ፡፡

፫. እስመ ኢይደልዎ ለክርስቲያን ይስማዕ ማኅሌተ ወመሰንቆ ወዕንዚራ ዘከመ ይገብሩ አብዳን ሕዝብ፡፡

፬. ወዓዲ ኢይዝክሩ ስመ አማልክት ወጣዖት በአፉሆሙ ወኢይስምይዎሙ ለሰይጣን ወለመላእክቲሁ እስመ ሶበ ይሰምዩ ስሞ ይሴስል እምኔሆሙ መንፈስ ቅዱስ ወየኀድር ህየንቴሁ መንፈስ ርኩስ ላዕሌሆሙ፡፡

### አንቀጽ ፳ ወ፰

በእንተ ከመ ኢመፍትው ክርስቲያን ይምሐሉ በስመ አማልክት ወአጋንንት ወግሙራ ኢይዝክርዎሙ ዘከመ ትካት ልማድ፡፡

፩. የምትወደዱ ወንድሞች ሆይ፣ ዘፈንን ከማድመጥና ከጨዋታ ነገር፣ ከተድላ ደስታና ከመባልዕት ጣዕም፣ ረብህ ጥቅም ከሌለው ከብላሽ ሥራም ሁሉ ትርቁ ዘንድ በጎ ምክርን እንመክራችኋለን ፡፡

፪. የሥጋችሁን ፈቃድ በቀን ለተድላ አታድርጉ፣ ነቢይ በመፍራት ለእግዚአብሔር ተገዙ፣ በመንቀጥቀጥም በሱ ደስ ይበላችሁ ብሏልና፡፡

፫. አላዋቆች ሕዝብ እንደሚያደርጉት ለክርስቲያን ዘፈንን መሰንቆን መለከትን ይሰማ ዘንድ አይገባውምና፡፡

፬. ዳግመኛም የአማልክትን የጣዖታትን ስም በአፋቸው አይጥሩ፣ ሰይጣንንና መላእክቱንም አይጥሩአቸው፣ ስሙንም በጠሩ ጊዜ መንፈስ ቅዱስ ከነርሱ ይለያልና፣ በእርሱ ፈንታም መንፈስ ርኩስ በላያቸው ያድራል፡፡

### ሀያ ስምንተኛ አንቀጽ

ክርስቲያን በጣዖታትና በአጋንንት ስም ይምሉ ዘንድ ፈጽመውም እንደ ቀድሞው ልማድ ስማቸውን ይጠሯቸው ዘንድ እንዳይገባ ይናገራል፡፡

፭. ኢመፍትው ንሕነ ክርስቲያን ንምሐል በስመ አማልክት ወኢን ዝክር አስማቲሆሙ በአፉነ ወኢ ንስግድ ሎሙ ወኢንፍርሆሙ እስመ ዘይገብር ከመዝ ወይገኒ ለአማልክት ይከውን ርኁቀ እም እግዚአብሔር ገባሬ ሕይወት፡፡

፮. ወባሕቱ እሉስ ኢኮኑ አማል ክተ አላ ዳዕሙ ግብረ እደ ሰብእ ወመናፍስተ ሰይጣን፡፡

፯. እስመ ይቤሎሙ እግዚአብሔር ለደቂቀ እስራኤል መነኑኒ ወመ ሐሉ በአማልክተ ነኪር ወአም ዕዑኒ በአማልክቲሆሙ፡፡[፩]

፰. እስመ ምኑን ወጽሉዕ ወርኩስ በውስተ መጻሕፍት ኵሉ ዘይሰ ግድ ወይገኒ ለአማልክት ወዘይም ሕል በስሞሙ ፡፡

፱. ወአኮሰ እሉ ባሕቲቶሙ አላ ዓዲ ረዐይተ ኮከብ ወመሰግላን ወእለ ያጣዕዉ ፡፡

፲. ወለእሉኒ ኢታምልክዎሙ ወኢ ትስግዱ ሎሙ ፡፡

፲፩. ወዓዲ ይቤ ነጺረከ ሰማየ ኢትስ ግድ ለፀሐይ ወለወርኀ ወለከዋክብት፡፡

፲፪. ኢትሑሩ እንከ ፍናተ አሕዛብ ወኢትትመሀሩ ምግባሮሙ ወኢት ፍርሁ እምትእምርተ ሰማይ ፡፡

፩. ዘዳግ. ፴፪ ፥ ፳፩

፭. እኛ ክርስቲያን በጣዖት ስም እንምል ዘንድ፣ በአፋችንም ስማቸ ውን እናነሣ ዘንድ፣ ፈርተናቸውም እንሰግድላቸው ዘንድ አገባብ አይደ ለም፤ እንደዚህ የሚያደርግ ለጣዖታት የሚገዛ ሰው ሕይወትን ከሚያደርግ ከእግዚአብሔር የራቀ ይሆናልና፡፡

፮. ነገር ግን እሊህ አማልክት አይ ደሉም፤ የሰይጣን መናፍስትና የሰው እጅ ሥራዎች ናቸው እንጂ፡፡

፯. እግዚአብሔር የእስራኤል ልጆ ችን ናቁኝ በሌላም አማልክቶች ማሉ በአማልክቶቻቸውም አሳዘ ኑኝ ብሏቸዋልና፡፡

፰. ለጣዖት የሚገዛና የሚሰግድ፣ በስማቸውም የሚምል ሁሉ፣ በመጻሕፍት ውስጥ የተናቀ የተጠላ ርኩስ ስለሆነ ፡፡

፱. እሊህ ብቻ አይደሉም ዳግመኛም ኮከብ የሚቈጥሩ፣ ጠንቋዮች ጣዖትን የሚያመልኩ ናቸው እንጂ ፡፡

፲. እለዚህንም አታምልኳቸው አት ስገዱላቸው ፡፡

፲፩. ዳግመኛም ሰማይን አይተህ ለፀ ሐይ ለጨረቃ ለከዋክብት አትስገድ፡፡

፲፪. የአሕዛብ ጐዳናን ሥራቸውንም አትማሩ፣ ከሰማይ ምልክት የተነ ሣም አትፍሩ ፡፡



፲፫. እስመ ፈጠረ ፀሐየ ወወርኀ ወከዋክብተ ያብርሁ ላዕለ ሰብእ ወአኮሰ ከመ ይስግዱ ሎሙ ፡፡

፲፬. እስመ እስራኤል ሰገዱ በገዳም ለግልፎ ስብኮ ላህም ወዓዲ አም ለኩ ፀሐየ ወከዋክብተ ፡፡

፲፭. በከመ ይቤ ሕዝቅኤል እንስሳ እለ ኢይነቡ ገብሩ ሎሙ አማልክተ፡፡

፲፮. ወከማሁ ግብፃውያን ሰገዱ ለብዙኃን አማልክት ወለገጸ ከልብ ወለአማልክት ዘወርቅ ወዘብሩር ዘይሁዳ ፡፡

፲፯. በከመ ይቤ እግዚአብሔር በአፈ ነቢይ አማልክቲሆሙ ለአሕዛብ ዘወ ርቅ ወዘብሩር ግብረ እደ እጓለ መሕ ያው አፍ ቦሙ ወኢይነቡ፣ ዐይን ቦሙ ወኢይሬእዩ፣ ዕዝነ ቦሙ ወኢ ይሰምዑ፣ አንፍ ቦሙ ወኢያጼንዉ፣ እድ ቦሙ ወኢይገሡ፣ እግር ቦሙ ወኢየሐውሩ፣ ወኢይነቡ በጐራዒ ቶሙ፣ ወአልቦ መንፈስ ውስተ አፉ ሆሙ፣ ከማሆሙ ለይኩኑ ኵሎሙ እለ ገብርዎሙ ወኵሎሙ እለ ይትዌከሉ ቦሙ፡፡[፪]

፲፰. ናሁ ሰማዕክሙ አፍቁራን አኃው ዘይቤ እግዚአብሔር ከመ እኩያን ወርኩሳን እሙንቱ እለ ያመል ክዎሙ ለአማልክት ወይሰግዱ ለፀ ሐይ ወለወርኀ ወለከዋክብት ፡፡

፲፫. ፀሐይንና ጨረቃን ከዋክብትንም የፈጠረ በሰው ላይ ያበሩ ዘንድ ነው እንጂ፣ ሊሰግዱላቸው አይደለምና፡፡

፲፬. እስራኤል በላም አምሳል ለተሠራ ጣዖት በገዳም ሰግደዋልና ዳግመኛም በፀሐይና በከዋክብት አመለኩ፡፡

፲፭. ሕዝቅኤል የማይናገሩ እንስሳትን ለራሳቸው አማልክትን አደረጉ እንዳለ፡፡

፲፮. እንደዚሁም ግብፃውያን ለብዙ አማልክት በውሻ አምሳል ለተሠሩ ከወርቅ ከብር ለተሠሩ ለይሁዳ ጣዖታት ሰገዱ፡፡

፲፯. እግዚአብሔር በነቢዩ ቃል የአ ሕዛብ ጣዖቶች ከወርቅ ከብር የተ ሠሩ የሰው እጅ ሥራዎች ናቸው፤ አፍ አላቸው አይናገሩም፤ ዓይን አላ ቸው አያዩም፤ ጆሮ አላቸው አይሰ ሙም፤ አፍንጫ አላቸው አያሸቱም፤ እጅ አላቸው አይዳስሱም፤ እግር አላ ቸው አይሄዱም በጉሮሮቻቸውም፣ አይ ናገሩም ፣ በአፋቸውም ውስጥ ቃል የለም፣ የሠሯቸውም ሁሉ የሚያም ኑባቸውም ሁሉ እንደነሱ ይሁኑ እንዳለ፡፡

፲፰. ተወዳጆች ወንድሞቼ ሆይ ጣዖ ታትን የሚያመልኩ ለፀሐይ ለጨ ረቃ ለከዋክብትም የሚሰግዱ እሊህ ርኩሳን ክፉዎች እንደሆኑ እግዚአ ብሔር ያለውን እነሆ ሰማችሁ ፡፡

፲፭. ወባሕቱ መፍትው ክርስቲያን መፍቀርያነ እግዚአብሔር ኢይም ሐሉ በፀሐይ ወበወርኀ ወከዋክ ብተ ሰማይ ወኢበምድር ::

፲፮. ወለነሰ አዘዘነ መምህርነ ኢንም ሐል ግሙራ ወኢበምንትኒ ናሁኬ ይከውን ቃልነ ጥዩቀ::

፲፯. እስመ ይቤ አግዚእነ ኢትም ሐሉ በሰማይ እስመ መንበሩ ለእግዚአብሔር ውእቱ ::

፲፰. ወኢ በምድር እስመ መከየደ እገሪሁ ይእቲ::

፲፱. ወኢ በኢየሩሳሌም እስመ ሀገሩ ለንጉሥ ዐቢይ ውእቱ::[፫]

፳. ወኢትምሐል በርእስከ እስመ አብዳን አይሁድ ይምሕሉ በርእሶሙ::

፳፩. እስመ ውእቱ አዘዘ ይኩን ቃሎሙ ለመሃይምናን እመኒ እወ እወ፣ ወእመኒ አልቦ አልቦ፣ ወዘሰ ይዌስክ ዲበዝ እኩይ ውእቱ::

፳፪. እስመ ዘይምሕል በሐሰት ይትዓደው ፍትሐ ወያከብሮሙ ለአማልክት ከመ ጻድቅ ::

፳፫. ወዘአስሐቶሙ እግዚአብሔር በዑረተ ልቦሙ ወበእከየ ምግባ ሮሙ ይገብሩ ዘኢይደሉ ::

፲፭. ነገር ግን የእግዚአብሔር ወዳ ጆች ክርስቲያኖች በፀሐይ በጨረቃ በሰማይ በክዋክብት በምድርም እን ዳይምሉ አገባብ ነው::

፲፮. እኛንስ በምንም ፈጽመን እን ዳንምል መምህራችን አዘዘን ፣ ነገ ራችን እነሆ የተረዳ ይሆናልና ::

፲፯. ጌታችን በሰማይ አትማሉ የእግ ዚአብሔር ዙፋኑ ስለሆነ ብሏልና::

፲፰. በምድርም አትማሉ የእግሩ መመላለሻ ናትና ::

፲፱. በኢየሩሳሌምም አትማሉ የታ ላቁ ንጉሥ አገር ናትና::

፳. በራስህም አትማል፣ አላዋቆች አይሁድ በራሳቸው ይምላሉና ::

፳፩. የምእመናን ነገራቸው እውነ ቱን እውነት፣ ሐሰቱን ሐሰት ማለት ይሆን ዘንድ አዝዟልና፤ ከዚህ በላይ የሚጨምር ግን ክፉ ነው ::

፳፪. በሐሰት የሚምል ሰው ፍር ድን ይደፋፈራል፣ አማልክትንም እንደ እውነተኛ ያከብራቸዋልና ::

፳፫. እግዚአብሔር ስሕተትን ያሳደ ረባቸው በልባቸው ድንቍርና በሥራ ቸው ክፋት የማይገባውን ይሠራሉ::

፫. ማቴ. ፭፡ ፴፮—፴፰



አንቀጽ ፳ወ፱

በእንተ ከመ መፍትው ይዕቀቡ ወይ ፈጽሙ ዕለተ በዓላት በፍሥሓ መንፈሳዊት::

፩. ኦ ፍቁራኒሁ ለእግዚአብሔር ዕቀቡ እንከ ዕለተ በዓላት ::

፪. ቀዳሚ በዓል ዘውእቱ ዕለተ ልደቱ ለክርስቶስ አመ ፳ወ፭ ለታ ስዕ ወርኅ በኍልቈ ሐሳበ ዕብራ ውያን፣ ወበኍልቈ ሐሳበ ግብፃ ውያን አመ ፳ወ፱ ለታኅሣሥ ዘው እቱ ራብዓይ ወርኅ::

፫. ወእምድኅረዝ አክብሩ በዓለ ኤጲፋንያ ዘቦቱ አስተርአየ እግ ዚአ ስብሐት መለኮቶ በውስተ ጥምቀቱ በኀበ ዮሐንስ በውስተ ፈለገ ዮርዳኖስ ::

፬. ወግበሩ በዐሥራይ ወርኅ አመ ሰዱስ በኍልቈ ሐሳበ ዕብራውያን::

፭. ወበኍልቈ ሐሳበ ግብፃውያንሰ አመ ፲ወ፩ ለወርኀ ጦቢ ዘውእቱ ጥር በኃምስ ወርኅ::

፮. ወእምድኅሬሁ ዕቀቡ በንጽሕ ፵ዓ ዕለተ ጾም ቅድስት::

፯. እንተ ይእቲ ትሜህረነ ጽሙና ወትዕግሥተ ጾመ ወጸሎተ ዘታቀ ርበነ ኀበ እግዚአብሔር ::

ሀያ ዘጠነኛ አንቀጽ

የበዓላትን ቀን በመንፈሳዊ ደስታ ይጠብቁ ዘንድ እንዲገባ ይና ገራል::

፩. እግዚአብሔርን የምትወዱ ወንድ ሞቼ ሆይ የበዓላትን ቀን ጠብቁ::

፪. መጀመሪያው በዓል ይኸውም ክርስቶስ የተወለደበት ቀን በዕብራ ውያን አቈጣጠር በዘጠኝኛው ወር በ፳፭ኛው ቀን ነው፣ በግብጻውያን አቈጣጠር በአራተኛው ወር በታኅ ሣሥ በ፳፱ ቀን ነው ::

፫. ከዚህ በኋላ የክብር ባለቤት ጌታ በዮሐንስ ዘንድ በተጠመቀበት በዮ ርዳኖስ ወንዝ መለኮቱን ያሳየበት ኤጲፋንያ የተባለ በዓለ ጥምቀትን አክብሩ ::

፬. በዕብራውያን አቆጣጠር ባስረኛው ወር በስድስተኛው ቀን አድርጉ::

፭. በግብጻውያን አቆጣጠር ግን ጦቢ በሚባለው በአምስተኛው ወር በጥር በአሥራ አንደኛው ቀን አድርጉ::

፮. ከዚህ በኋላ የከበረች አርባዋን የጾም ቀን በንጹሕ ጠብቁ ::

፯. ይህችውም ወደ እግዚአብሔር የምታቀርበን ጾምን፣ ጸሎትን፣ ጽሙ ናን፣ ትዕግሥትን የምታስተምረን ናት::

፰. ወትትፌጸም ዛቲ ጾም ቅድስት በዕለተ ፋሲካ ዘቦቱ ኮነ መድኃኒትነ።

፱. ባሕቱ ይከውን ቀዳሚ ጾምክሙ በሰኑይ ዕለት በቅድመ ፋሲካ ።

፲. እስመ በሳኒታ ሆሣዕና በሰኑይ ዕለት ተጋብኡ ዕልዋነ ሃይማኖት ወሕግ እኩያን አይሁድ፣ ወተማከሩ ላዕለ እግዚእ፣ ወቀዳሚ ወርኀ ብሩህ ዘውእቱ ሚያዝያ ።

፲፩. በሠሉስ ዕለት ወሰኩ ወአፈድፈዱ ምክረ ።

፲፪. ወበረቡዕ ዕለት ፈጸሙ ምክረ ከመ ያግብእዎ ለሞት በዲበ መስቀል።

፲፫. ወይሁዳሰ አእመረ ዘንተ ምክሮሙ እስመ ሰራቂ ውእቱ እምአሚሃ አውደቆ ሰይጣን በፍቅረ ንዋየ ወርቅ፣ እስመ መባአ አስክሬን የዐቅብ ውእቱ ወይቀስጥ ንዋየ ነዳያን።

፲፬. ወዘንተ ኵሎ ገቢሮ ኢሰደዶ እግዚእ እስመ የአምር እከየ ልቡ ።

፲፭. ወአኀዘ ይብላዕ ምስሌሁ ፈቂዶ እግዚእ ይገሥጾ ወናሁ አለበወነ ከመ ውእቱ ያገብኦ ።

፰. ይህችም የከበረች ጾም ድኅነታችን በሆነበት በፋሲካ ቀን ትጨረሳለች።

፱. ነገር ግን የጾማችሁ መጀመሪያ ከፋሲካ አስቀድሞ ሰኞ ቀን ይሁን።

፲. በሆሣዕና ማግሥት ሰኞ ቀን ሕግንና ሃይማኖትን የካዱ ክፉዎች አይሁድ ተሰብስበው በጌታ ላይ ተማክረዋልና፣ ይኸውም ብሩህ በሆነ በመጀመርያው ወር በሚያዝያ ነው።

፲፩. ማክሰኞ ቀን ምክርን ጨመሩ አጸኑ ።

፲፪. በረቡዕ ቀን በመስቀል ላይ ለሞት አሳልፈው ይሰጡት ዘንድ ምክርን ፈጸሙ ።

፲፫. ይሁዳ ግን ይህን ምክራቸውን ዐወቀ፣ ሌባ ነበርና፣ ከዚያን ጊዜ ወዲህ ገንዘብ በመውደድ ሰይጣን ድል አደረገው፣ ወደ ጥራት የሚገባውን መባዕ እርሱ ይጠብቅ ነበርና የድኆችንም ገንዘብ ይነጥቅ ነበር።

፲፬. ይህን ሁሉ አድርጎ ጌታ አላሳደደውም የልቡናውን ክፋት ስለ አወቀ።

፲፭. ከርሱ ጋራ ይበላ ጀመር፣ ጌታ ይመክረው ዘንድ ወደ እርሱ አሳልፎ እንደሚሰጠውም አስረዳን።



፲፮. ወበእንተዝ ይቤ አሜን እብለክሙ ከመ አሐዱ እምኔክሙ ያገብአኒ ።

፲፯. ወተበሃልነ በበይናቲነ ፩ ፩ እንዘ ንብል አነኑ እግዚኦ እንጋ ።

፲፰. ወተንሣእኩ አነ ፩ዱ እም፲ ወ፪ እስመ ውእቱ ያፈቅር ኪያየ እምኵሎሙ አርድእት ተሰአልክዎ ወእቤሎ እግዚኦ መኑ ዘያገብአከ።

፲፱. ወእግዚእነሰ ኢነገረኒ ስሞ ወባሕቱ አመረኒ በ፪ቱ ትእምርታት።

፳. ዘቀዳሚ በእንተ ዘይቤ ዘይጸብሕ እዴሁ ምስሌየ ውስተ መጽብሕ።

፳፩. ወደገመ ወይቤ ዘእሜጥዎ አነ ኀብስተ ውእቱ ያገብአኒ እስመ ይቤሎ አነኑ ውእቱ እግዚኦ ።

፳፪. እግዚእነሰ ኢይቤሎ እወ አንተ አላ ዳዕሙ አንተ ትቤ።

፳፫. ውእቱሰ ኢፈቀደ ያግህድ ሎቱ ዳዕሙ ይቤሎ እምኀየሶ ለውእቱ ብእሲ ሶበ ኢተወልደ ዘበእደዊሁ ይትሜጠውዎ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ።

፳፬. ወሰሚያ ዘንተ ይሁዳ ሖረ ኀበ ሊቃነ ካህናት ወይቤሎሙ ምንተ ትሁቡኒ ወአነ አገብኦ ለክሙ ወተማከሩ የሀብዎ ሠላሳ ብሩረ ።

፲፮. ስለዚህም ከናንተ አንዱ እንደሚያሲይዘኝ በእውነት እነግራችኋለሁ አለ ።

፲፯. እርስ በርሳችን እየአንድ አንዳችን አቤቱ እንጃ እኔን ነኝ ? እኔን ነኝ? ተባባልን ።

፲፰. ከአሥራ ሁለቱ አንዱ እኔ ተነሣሁ፣ ከአርድዕት ሁሉ እርሱ እኔን ይወዳልና አቤቱ ማነው? የሚያሲዝህ ብዬ ጠየቅሁት ።

፲፱. ጌታችን ግን ስሙን አልነገረኝም በሁለት ምልክቶች አመለከተኝ እንጂ።

፳. የመጀመሪያው እጆቹን ከኔ ጋራ ከወጡ ውሥጥ የሚጠልቀው ያለው ነው።

፳፩. እኔ በእንጀራው ከወጡ ጠልቄ የምሰጠው እርሱ ያስይዘኛል ያለው ነው፤ እርሱ አቤቱ እኔ ነኝን ብሎታልና።

፳፪. ጌታችን ግን አዎን አንተ ነህ አላለውም፣ አንተ ትላለህ አለው እንጂ።

፳፫. እርሱ ግን ሊገልጽለት አልወደደም ወልደ ዕጓለ እመሕያው ጌታን በእጆቹ አሳልፎ የሚሰጥ ለዚያ ሰው ባልተወለደ በተሻለው ነበረ አለው እንጂ ።

፳፬. ይሁዳ ይህንን ሰምቶ ወደ ሊቃነ ካህናቱ ዘንድ ሄዶ እኔ ለናንተ አስይዘዋለሁ፤ ምን ትሰጡኛላችሁ? አላቸው፤ ሠላሳ ብር ይሰጡት ዘንድ ተማከሩ።

፳፭. ውእተ አሚረ ኃሙስ ዕለት አመ በልዐ ፍሥሐ እግዚእነ ምስሌነ::

፳፮. ወይሁዳ ነሥአ ኅብስተ ወጸብሐ እደዊሁ ውስተ መጽብሕ ወወፅአ ሌሊተ::

፳፯. ወይቤለነ እግዚእነ በጽሐት ሰዓት ናሁ ትዘረዉ ኵልክሙ ወተኃድጉኒ ወንቤ ፩ ፩ እምኔነ ኢነኃድገከ ::

፳፰. ወእቤ አነ ጴጥሮስ ለእመ ኵሎሙ ኀደጉከ አንሰ ኢየኀድገከ እመውትሂ ምስሌከ ::

፳፱. ወይቤለኒ አሜን እብለከ ትክህደኒ ሥልሰ ዘእንበለ ይንቁ ዶርሆ ከመ ዘኢተአምረኒ ::

፴. ናሁ ለበውነ ዘንተ ምሥጢረ ቅድሳት ዘውእቱ ሥጋሁ ቅዱስ ወደሙ ክቡር እንዘ ሀሎ ይሁዳ ምስሌነ::

፴፩. ወእምዝ ወፅአ እግዚእነ ውስተ ደብረ ዘይት ወንሕነኒ ሖርነ ምስሌሁ እንዘ ንጼሊ ወንባርክ በከመ ናለምድ ::

፴፪. ሕቀ ተአተተ እምኔነ ወጸለየ ኀበ አብ እንዘ ይብል ኦ አባ እመሰ ይትከሃል እምኔየ ይኅልፍ ዝንቱ ጽዋዕ ወባሕቱ ይኩን ፈቃድከ ወአኮ ፈቃደ ዚአየ ከመዝ ገብረ ሠለስተ ጊዜ ::

፳፭. ያን ጊዜም ጌታችን ከእኛ ጋራ ፋሲካን የበላበት አምስተኛ ቀን ነው::

፳፮. ይሁዳም እንጀራውን ይዞ በእጆቹ ከወጡ ጠልቆ በሌሊት ወጣ ::

፳፯. ጌታችን ሰዓቲቱ ደረሰች፣ እነሆ እኔን ትታችሁኝ ሁላችሁም ትበተናላችሁ አለን፣ ከኛ ወገን እየአንድ አንዳችን አንተውህም አንተውህም አልነ::

፳፰. እኔ ጴጥሮስ ሁሉ ቢተዉህ እኔ አልተውህም፣ ካንተ ጋራ እሞታለሁ አልኩት ::

፳፱. ዶሮ ሳይጮህ እኔን እንደ ማታውቀኝ ሦስት ጊዜ ትክደኛለህ ብዬ በእውነት እነግርሃለሁ አለኝ::

፴. ይሁዳ ከኛ ጋራ ሳለ ቅዱስ ሥጋው ክቡር ደሙ የሆነ ይህን የከበረ ምሥጢር እነሆ ዓወቅነ ::

፴፩. ከዚህ በኋላ ጌታችን ወደ ደብረ ዘይት ወጣ፣ እኛም እንደ አስለመድነው እያመሰገን እየጸለይን ከርሱ ጋራ ሄድነ ::

፴፪. ከኛ ጥቂት እልፍ ብሎ ወደ አብ እንዲህ ብሎ ጸለየ፣ አባቴ ሆይ እሚቻልስ ከሆነ ይህ ጽዋዓ ሞት ከኔ ይለፍ፣ ነገር ግን የአንተ ፈቃድ ይሁን እንጂ የእኔ ፈቃድ አይደለም፤ ሦስት ጊዜ እንዲህ ጸለየ::



፴፫. ወከብዳ አዕይንቲነ እምንዋም እንበይነ ኀዘን ::

፴፬. ወመጽአ ኀቤነ እግዚእነ ወይቤለነ በጽሐ ጊዜሁ ናሁ ያገብእዎ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ውስተ እደ ኃጥኣን::

፴፭. ናሁ መጽአ ይሁዳ ወብዙኃን ዕልዋን ምስሌሁ ወወሀቦሙ ስዕመተ ትእምርት በጕሕሉት እንተ ምልዕተ ዓመፃ በዘያገብኦ::

፴፮. ወለቢዎሙ ትእምርተ ዘወሀቦሙ ይሁዳ አኀዝዎ ለኢየሱስ፤ ወወሰድዎ አሲሮሙ ኀበ ቀያፋ ሊቀ ካህናት መካነ ኀበ አልቦ ሰብእ ኄራን ወኢቅዱሳን ካህናት አላ ዳዕሙ እኩያን ሕዝብ ወርኩሳን ካህናት እለ ውፁኣን እምሕግ ::

፴፯. ወእሙንቱሰ ኢያጽርዑ እንዘ ይፀርፉ ላዕሌሁ ወይጼዕልዎ ወይዘብጥዎ ወይወርቁ ውስተ ገጹ ወይሣለቅዎ ወይኰርዕዎ ርእሶ::

፴፰. ወየሐሥሡ ሎቱ ሰማዕተ ሐሰት፣ እንዘ ይብሉ ይነብብ ፅርፈተ ላዕለ ሙሴ፣ ወይነሥት ቤተ መቅደስ፣ ወያጸርዕ ጸባሕተ እምሰብአ ሮሜ ወየዐሉ ነገሥተ ወይሬሲ ርእሶ ንጉሠ ::

፴፫. ስለ ኃዘን ከእንቅልፍ የተነሣ ዓይኖቻችን ፈዘዙ ::

፴፬. ጌታችን ወደኛ መጥቶ እነሆ ወልደ ዕጓለ እመሕያው በኃጥአን እጅ የሚያዝበት ጊዜ ደረሰ አለን::

፴፭. ብዙ ወንጀለኞች ከርሱ ጋራ የተከተሉት ይሁዳ እነሆ መጣ፣ በደልን በተመላች ተንኰል የሚያሲዝበትን የመሳም ምልክትን ሰጣቸው::

፴፮. ይሁዳ የሰጣቸውንም ምልክት አስተውለው ጌታችን ኢየሱስን ይዘው አሥረው ወደ ካህናቱ አለቃ ወደ ቀያፋ ወሰዱት፣ ደጋግ ሰዎችና ቅዱሳን ካህናት ወደሌሉበት ቦታ፤ ክፋዎች ወገኖች ከሕግ የወጡ ርኩሳን ካህናቶች ናቸው እንጂ ::

፴፯. እነርሱም በእርሱ ላይ ሲሳደቡ ሲያሽሟጥጡት፣ ሲመቱት፣ ምራቃቸውን በፊቱ ሲተፉ፣ ሲዘብቱ፣ ራሱንም ሲመቱት አላቋረጡም ::

፴፰. የሐሰት ምስክሮችን ፈለጉ፣ በሙሴ ላይ ስድብን ይናገራል፣ ቤተ መቅደስን ያፈርሳል ፣ ከሮም ሰዎች ወገን ግብርን ይከለክላል፣ ነገሥታቱንም ይከዳል፣ ራሱን ንጉሥ ያደርጋል እያሉ ::

፴፱. ዘንተ ኵሎ ገብሩ ላዕሌሁ ከለባት ብዙኃን ወአስዋር ሥቡሓን እለ አልቦሙ ምሕረት::

፵. ወሌሊተ አውፅእዎ ወወሰድዎ ኀበ ሐና ሐሙሁ ለቀያፋ ወገብሩ ላዕሌሁ ብዙኀ እከየ ወአግብእዎ ኀበ ጲላጦስ መኰንነ ሮሜ ::

፵፩. ወአሜሃ ዓርብ ዕለታ ወአስተዋደይዎ በብዙኀ ግብር ዘኢመፍትው ነጽሮቱ ::

፵፪. ወሰሚያ ጲላጦስ መኰንነ ሮሜ ኢአምኖሙ አላ ይቤሎሙ ኢረከብኩ በላዕለዝ ብእሲ ጌጋየ በዘይመውት ::

፵፫. ወእምዝ አምጽኡ ሎቱ ፪ተ ሰማዕተ እለ ይብሉ ወይነቡ ሐሰተ ላዕለ ክርስቶስ::

፵፬. ወአእመረ ጲላጦስ ስምዖሙ ከመ ኢኮነ ብሩህ ወእሙንቱሰ ተመይጡ ወመከሩ ምክረ በዘያፈርህዎ ለጲላጦስ::

፵፭. ወይቤሉ ብእሲ ይሬሲ ርእሶ ንጉሠ ወይከልአነ ተቀንዮ ለንጉሥ::

፵፮. ሐሰዉ ወፈትሑ ላዕሌሁ በዐመፃ ከልሐ ወይቤሉ ስቅሎ ስቅሎ::

፵፯. ከመ ይትፈጸም ላዕሌሁ ቃለ ነቢይ ዘይቤ ተንሥኡ ላዕሌየ ሰማዕተ ዓመፃ ወዘኢየአምር ነበቡ ላዕሌየ ፈደዩኒ እኪተ ህየንተ ሠናይት ::

፴፱. ብዙ ውሾች፣ ምሕረት የሌላቸው የሰቡ ክብቶች አይሁድ፣ በርሱ ላይ ይኽን ሁሉ አደረጉ ::

፵. በሌሊት አውጥተው ወደ ቀያፋ አማች ወደ ሐና ወሰዱት፣ በእርሱ ላይ ብዙ ክፉ ሥራ ሠርተው ወደ ሮም ገዥ ወደ ጲላጦስ መለሱት::

፵፩. ያን ጊዜ ቀኑ ዓርብ ነው፤ መታየቱ በማይገባ በብዙ ሥራ አሳጡት ::

፵፪. የሮም ገዥ ጲላጦስ ሰምቶ አላመናቸውም፣ ነገር ግን በዚህ ሰው ላይ የሚሞትበትን በደል አላገኘሁበትም አላቸው ::

፵፫. ከዚህ በኋላ በክርስቶስ ላይ ሐሰትን ይናገራሉ የሚባሉ ሁለት የሐሰት ምስክሮችን አመጡበት ::

፵፬. ጲላጦስም ምስክርነታቸው አንድ እንዳልሆነ ዓወቀ፣ እነርሱ ግን ተመልሰው ጲላጦስን በመፍራት የፍርሃት ምክርን መከሩ::

፵፭. ይኼ ሰው እራሱን ንጉሥ ያደርጋል፤ ለንጉሥም መገዛትን ይከለክለናል አሉ::

፵፮. በእርሱም ላይ ሐሰትን ተናግረው የበደል ፍርድን ፈረዱ፣ ስቀለው ስቀለው ብለውም ጮሁ ::

፵፯. የሐሰተ ምስክሮች በኔ ላይ ተነሡ፤ የማላውቀውንም በኔ ላይ ተናገሩ፣ ስለ በጐ ፈንታ ክፋውን መለሱልኝ ያለው የነቢዩ ቃል በእርሱ ላይ ይፈጸም ዘንድ ::



፵፰. ወካዕበ ይቤ ዐገቱኒ ከለባት ብዙኃን ወአኀዙኒ ማኅበሮሙ ለእኩያን ::

፵፱. ወሶበ ስዕነ ጲላጦስ አድኅኖቶ ለኢየሱስ ክርስቶስ እምፍርሀቶሙ ለአይሁድ መከረ ይግበር ፈቃዶሙ ለሕዝብ ::

፶. እስመ ቀዲሙ ስምዐ ኮነ ጲላጦስ ወይቤ አልቦ ዘረከብኩ ሎቱ ጌጋየ በዘይመውት ::

፶፩. ወአይሁድሰ እኩያን ሰቀልዎ ዲበ መስቀል ወቀነውዎ ::

፶፪. ወለሮምስ ቦሙ ሥርዐት ወኢይቀትሉ ወኢመነሂ ዘእንበለ ይትመዋእ በፍትሐ በኀበ መኰንን::

፶፫. ወባሕቱ ሐራ ሰገራት ነሥእዎ ለእግዚአ ስብሐት ወጊዜ ፫ቱ ሰዓት አዕረግዎ ዲበ ዕፅ ወበጊዜ ፮ ሰዓት ሰቀልዎ ::

፶፬. ወአስተይዎ ብኂዐ ከርቤ ቱሱሐ ዘምስለ ሐሞት ነሥኡ አልባሲሁ ወተካፈሉ በበይናቲሆሙ::

፶፭. ወሰቀሉ ምስሌሁ ገባርያነ እኪት ፪ዔ፤ አሐደ በየማኑ ወአሐደ በጸጋሙ::

፶፮. ከመ ይትፈጸም ዘጽሑፍ ዘይብል ወወደዩ ሐሞተ ውስተ መብልዕየ ወአስተዩኒ ብሒዐ ለጽምዕየ::

፵፰. ሁለተኛም ብዙዎች ውሾች ከበቡኝ ፣ የክፉዎች ማኅበሮችም ያዙኝ አለ ::

፵፱. አይሁድን ከመፍራት የተነሣ ጲላጦስ ኢየሱስ ክርስቶስን ማዳን በተሳነው ጊዜ የሕዝቡን ፈቃዳቸውን ያደርግ ዘንድ መከረ ::

፶. ይሙት በቃ የሚያስፈርድበት በደልን ያገኘሁበት የለም ብሎ ጲላጦስ አስቀድሞ ምስክርን ሆኗልና::

፶፩. ክፉዎች አይሁድ ግን በመስቀል ላይ ሰቅለው ቸነከሩት ::

፶፪. ለሮማውያን ግን ሥራት አላቸው፣ ከዳኛው ዘንድ በፍርድ ሳይረታ ማንንም አይገድሉም::

፶፫. ነገር ግን የጭፍሮች አለቆች የክብር ባለቤት ጌታን በ፫ ሰዓት በእንጨት መስቀል ላይ አውጥተው በ፮ ሰዓት ሰቀሉት ::

፶፬. ከርቤውን ከሐሞት ጋራ ቀላቅለው አጠጡት፣ ልብሶቹንም ወስደው እርስ በርሳቸው ተካፈሉት::

፶፭. ከርሱ ጋራም ሁለቱን ክፉ አድራጊዎች አንዱን በቀኙ አንዱን በግራው ሰቀሉ ::

፶፮. በመብሌ ውስጥ ሐሞትን ጨመሩ ለጥማቴም መፃፃን አጠጡኝ ተብሎ የተጻፈው ይፈጸም ዘንድ ::

፶፯. ወካዕበ ይቤ ተዐፀወ ዲበ ዐራ ዝየ ::

፶፰. ወቦ ኀበ ይብል ተኰሰቈ ምስለ ገበርተ ዐመፃ ::

፶፱. ወእምዝ ኮነ ጽልመት ፫ ሰዓተ እምስድስቱ ሰዓት እስከ ተሱዓት ሰዓት::

፷. ወእምዝ ሰሰለ ጽልመት ወአስ ተርአየ ብርሃን በከመ ጽሑፍ፣ ኮነ መዓልት ሌሊተ ወአስተርአየ ብርሃን በምሴት::

፷፩. ወጊዜ ተሱዓት ሰዓት ገዐረ ኢየ ሱስ በዐቢይ ቃል ወይቤ ኤሎሄ ኤሎሄ ላማ ሰበቅታኒ፣ ዘበትርጓሜሁ አምላ ኪየ አምላኪየ ለምንት ኀደገኒ::

፷፪. ወእምዝ ጸርሐ ወይቤ ኦ አባ ሥረይ ሎሙ እስመ በዘኢየአምሩ ይገብሩ ::

፷፫. ወካዕበ ይቤ ኦ አባ አመሐፅን ነፍስየ ውስተ እዴከ::[1]

፷፬. ወእምዝ አጽነነ ርእሶ፣ ወወጽ አት መንፈሱ ወአውረድዎ እምዲበ መስቀል ወቀበርዎ ውስተ መቃብር ሐዲስ ::

፷፭. ወመስዮ ለጸቢሐ ሠርከ ሰን በት ተንሥአ እሙታን፣ ወፈጺሞ ኵሎ ዘነገረነ እምቅድመ ይሕምም ከመ ይነብር ወልደ ዕጓለ እመሕ ያው ውስተ ከርሠ ምድር ሠሉሰ መዋዕለ ወሠሉሰ ለያልየ ::

፶፯. ሁለተኛም በልብሱ ላይ ዕጣ ተጣጣሉ አለ ::

፶፰. በደልን ከማያደርጉ ጋራ ተቈ ጠረ የሚልም አለ ::

፶፱. ከዚህም በኋላ ከስድስት ጀምሮ እስከ ዘጠኝ ሰዓት ድረስ ሦስት ሰዓት ጨለማን ሆነ ::

፷. ከዚህም በኋላ ጨለማው ለቀቀ፣ ብርሃንም ታየ፣ መዓልት ሌሊትን ሆነ ተብሎ እንደተጻፈ በሠርክም ብርሃን ታየ ::

፷፩. ጌታችንኢየሱስ ክርስቶስ በት ልቅ ቃል ኤሎሄ ኤሎሄ ላማ ሰብቅታኒ ብሎ ጮኸ፣ ትርጓሜውም አምላኬ አምላኬ ለምን ተውከኝ ማለት ነው ::

፷፪. ከዚህም በኋላ አባቴ ሆይ! የማያውቁትን ያደርጋሉና ይቅር በላቸው ብሎ ጮኸ ::

፷፫. ዳግመኛም አባት ሆይ ነፍ ሴን በእጅህ አደራ እሰጣለሁ አለ::

፷፬. ከዚህ በኋላ ራሱን ዘንበል አደረገ ፣ ነፍሱም ተለየች ፣ ከመስ ቀሉ ላይ አውርደው በአዲስ መቃ ብር ቀበሩት ::

፷፭. ቅዳሜ ማታ ከመሽ በኋላ ለእ ሑድ አጥቢያ፣ የሰው ልጅ ሦስት መዓልት ሦስት ሌሊት በከርሠ መቃ ብር እንዲያድር፣ መከራ ሳይቀበል የነገረንን ሁሉ ፈጽሞ ከሙታን ተለይቶ ተነሣ::

[1] ሉቃ. ፳፫. ፵፬–፵፯ ፤ ዮሐ. ፲፱–፲፰



፷፮. ወእምድኅረ ተንሥአ እሙ ታን አስተርአያ ቀዲሙ ለማርያም መግደላዊት፣ ወለማርያም እንተ ያዕ ቆብ፣ ወለወልደ ቀለዮጳ በፍኖት::

፷፯. ወእምድኅሬሁ አስተርአየነ ለነ ለአርዳኢሁ እንዘ ጉቡኣን ንሕነ በእ ንተ ፍርሀቶሙ ለአይሁድ፤ እስመ ዝንቱ ጽሑፍ ውስተ ወንጌል ::

፷፰. ወካዕበ አዘዘነ ንጹም ጾመ ቅድ ስት ፋሲካ ሰዱሰ ዕለተ በእንተ ዕል ወቶሙ ለዕልዋን ወእከዮሙ ለአ ይሁድ እለ ውፁኣን እምሕግ ::

፷፱. ወካዕበ ንጹም ረቡዐ ወዓርበ፣ ረቡዕሰ በእንተ ዘፈጸሙ ምክረ እኩየ ላዕሌሁ፣ ወዓርብኒ በእንተ ሕማማቲሁ መድኃኒት ::

፸. መፍትው ኢንጹም በሰንበት ዘእንበለ አሐቲ ዕለት እንተ ሕማም::

፸፩. ወባዕዳነሰ ሰንበታተ ናክብር እስመ አዕረፈ እግዚእነ አምኵሉ ግብሩ በዕለተ ሰንበት::

፸፪. እስመ መጽአ እግዚእ ወእሙ ንቱሰ ኢአምኑ ቦቱ ወኢተወክፉ ተግሣጸ፤ ወበእንተዝ ኀጕሉ መድ ኀኒቶሙ ::

፸፫. ወአንትሙሰ ብፁዓን ወዘመድ ቅዱስ፤ እስመ ኢኮንክሙ ከመ ዘት ካት ሕዝብ አላ ዳዕሙ ድኅንክሙ እምዕልወት ወአምልኮ ጣዖት::

፷፮. ከሙታን ተለይቶ ከተነሣ በኋ ላም ለመግደላዊት ማርያም፣ ለያዕ ቆብ እናት ማርያምና ለቀለዮጳም ልጅ በጐዳና አስቀድሞ ታያቸው::

፷፯. ከዚህ በኋላም እኛ አይሁድን ስለ ፈራን ተሰብስበን ሳለን ለደቀ መዛሙርቱ ታየን፣ ይህ በወንጌል ተጽፏልና ::

፷፰. ዳግመኛም የተለየች የፋሲካ ጾምን ፮ ቀን እንጾም ዘንድ አዘዘን፣ ስለ ከሃዲዎች ክህደትና ከሕግ ስለ ወጡ ስለ አይሁድ ክፋት::

፷፱. ዳግመኛም ዓርብ ረቡዕን እን ጹም፣ ረቡዕን በርሱ ላይ ክፉ ምክርን ስለ ፈጸሙ፣ ዓርብንም እኛ የምንድ ንበት መከራን ስለተቀበለበት ነው::

፸. በቀዳሚት ሰንበት እንዳንጾም መሆን አገባብ ነው፣ መከራን ከተ ቀበለባት ከቀዳም ሥዑር በቀር::

፸፩. ሌሎችን ሰንበቶች ግን እናክ ብር፣ ጌታችን በቀዳሚት ሰንበት ከሥ ራው ሁሉ አርፏልና::

፸፪. ጌታ መጥቷልና እነርሱ አላ መኑበትም ፣ ምክሩንም አልተቀበ ሉም፣ ስለዚህም የሚድኑበትን አጡ ::

፸፫. እናንተ ግን ልዩና ክቡር ዘመድ ናችሁ፣ ጣዖትን ከማምለክና ከክህ ደት ዳናችሁ፣ እንደቀድሞ ሕዝብ አይደላችሁምና ::

፸፬. አንትሙሰ ሕዝበ እግዚአብሔር፣ ወለክሙ ተርኅወ አናቅጸ ሕይወት እንዘ ቀዲሙ ጽሉዓን ወምኑናን አንትሙ::

፸፭. ወይእዜሰ ኮንክሙ ኅሩያኒሁ ወፍቁራኒሁ ሕዝብ ቅዱስ ለእግዚአብሔር እለ ድልዋን ትስብኩ መንክራቲሁ ለመድኀኒነ::

፸፮. እስመ ይቤ ረከቡኒ እለ ኢኃሠሡኒ ወአስተርአይኩ ለእለ ኢሐለዩኒ::

፸፯. ወእቤሎሙ ለሕዝብ ለእለ የአምሩ ስምየ ናሁ ኀሠሥክሙኒ ወአኮ አንትሙ ዘኃሠሥክሙኒ አላ ዳዕሙ አመንክሙ ብየ ወሰማዕክሙ ቤተ ክርስቲያንየ ወድኅንክሙ እምስሕተተ አማልክት ወተለውክምዎ ለእግዚአብሔር አብ አኃዜ ኵሉ ወወልዱ ኢየሱስ ክርስቶስ ወኮንክሙ ኍሉቃነ ምስለ እለ አምኑ ብየ እልፍ አእላፍ ወትእልፌተ አእላፋት::

፸፰. ወአንትሙሰ ኢኮንክሙ ከመ እስራኤል እለ ኢአምኑ ብየ ወበእንቲአሆሙ ይቤ ኵሎ አሚረ አነሥእ እደውየ ኀበ ሕዝብ ዐላውያን እለ ኢይሰምዑ ወኢይትኤዘዙ ወየሐውሩ ፍኖተ እኪተ እንተ ኢኮነት ሠናይተ::

፸፱. አላ ባሕቱ ሕዝብ ዘይተሉ ኃጢአተ ወያምዕዑኒ ወትረ::

፸፬. እናንተም የእግዚአብሔር ወገኖች ናችሁ፣ ቀድሞ የተናቃችሁና የተጠላችሁ ስትሆኑ ለእናንተ የሕይወት በሮች ተከፈቱላችሁ::

፸፭. ዛሬ ግን ለእግዚአብሔር የተለየ ምርጥ ወዳጆችና የመድኃኒታችን ታምራቶቹን ታስተምሩን ዘንድ የተዘጋጃችሁ ሆናችሁ::

፸፮. ያልፈለጉኝ አገኙኝ፣ ላላሰቡኝም ተገለጽኩ ብሏልና::

፸፯. ስሜን ለሚያውቁት ሕዝብም እነሆ ፈለጋችሁኝ፣ የፈለጋችሁኝም እናንተ አይደላችሁም አልኋቸው፤ በእኔ አመናችሁብኝ እንጂ በኔ ያመኑትን ምእመናኔንም ሰምታችሁ ከጣዖታት ስሕተት ዳናችሁ፣ ሁሉን የፈጠረ እግዚአብሔር አብንና ልጁን ኢየሱስ ክርስቶስን ተከትላችሁ በኔ ከአመኑ ከእልፍና እልፍ ጊዜ እልፍ ከሚሆኑ ጋራ የተቈጠራችሁ ሆናችሁ::

፸፰. እናንተ ግን እንዳላመኑብኝ እንደ እስራኤል አይደላችሁም ፣ ስለ እነርሱም ትእዛዜን ሰምተው ወደ አልታዘዙኝ ከሃዲዎች በጎ ያይደለች ክፉ ጐዳናንም ወደሚሄዱ ሰዎች ሁልጊዜ እጆቼን እዘረጋለሁ አለ ::

፸፱. ነገር ግን ኃጢአትን የሚከተሉ ሕዝቦች ሁልጊዜ ያስቆጡኛል::



፹. ርኢክሙኑ ከመ እሙንቱ ዐለውዎ ለእግዚአብሔር ወኢአምኑ ቦቱ::

፹፩. ወበእንተዝ ይቤ ከመ እለ አምዕዕዎ ለመንፈስ ቅዱስ ዖረ ልቦሙ ወተወሰከ ዲቤሆሙ መቅሠፍት በእከየ ሕሊናሆሙ::

፹፪. እስመ ይቤሉ ነአምን በክርስቶስ ወእሙንቱሰ ኢአምኑ ከመ ውእቱ እግዚአብሔር አምላክ ዘተወልደ እምአብ እምቅድመ ፍጥረት ወልድ ዋሕድ ቃለ አብ::

፹፫. ወእሙንቱሰ ሕፁፃነ ሃይማኖት ኢያእመርዎ ወኢለበዉ ትንቢተ ነቢያት ዘተጽሕፈ በእንቲአሁ ከመ ይትወለድ ክርስቶስ እምድንግል እንዘ ያነብቡ ወይሰምዑ ዘይቤ፣ ናሁ ድንግል ትፀንስ ወትወልድ ወልደ ወይሰመይ ስሙ አማኑኤል[፪] እስመ ሕፃን ተወልደ ለነ ወልድ ተውህበ ለነ ወቅድመት ኮነ ዲበ መትከፍቱ ወይሰመይ ስሙ ዐቢየ ምክር ወመልአከ ሰላም እስመ አነ አመጽእ ሰላመ ለመላእክት ወሕወይትሰ ዚአሁ ወዐበይ ቅድሜሁ ወአልቦ ማኅለቅት ለሰላሙ::[፫]

፹፬. ወበእከየ ምግባሮሙ እንተ አልባቲ ተፍጻሜት ወበእንተዝ ይቤ እግዚኦ መኑ የአምነነ ቃለነ ወለመኑ ተከሥተ መዝራዕትከ::

፹. እነርሱ እግዚአብሔርን እንዳላመኑበትና እንደ ካዱት አያችሁን?

፹፩. ስለዚህም መንፈስ ቅዱስን ያስቆጡት ሰዎች ልቡናቸው ደነቈረ፣ በሐሳባቸው ክፋትም መቅሠፍት ተጨመረባቸው አለ::

፹፪. በክርስቶስ እናምናለን ይላሉ፣ እነርሱ ግን የአብ አካላዊ ቃል ከፍጥረት ሁሉ አስቀድሞ ከእግዚአብሔር አብ የተወለደ ፈጣሪ እግዚአብሔር እንደሆነ አላመኑምና::

፹፫. እነርሱም ሃይማኖት የጐደላቸው ናቸው፣ ክርስቶስ ከድንግል እንዲወለድ ስለእርሱ በነቢያት የተጻፈውንም ልብ አላደረጉትም፣ እነሆ ድንግል ትፀንሳለች፣ ወንድ ልጅንም ትወልዳለች፣ ስሙም አማኑኤል ይባላል፣ ያለውን እየሰሙና እያነበቡ አላወቁም፣ ሕፃን ተወልዶልናልና፣ ወንድ ልጅም ተሰጥቶናልና፣ አለቅነትም በጫንቃው ላይ አለ፣ ስሙም ድንቅ መካር፣ የሰላም አለቃ ይባላል፣ እኔ ለአለቆች ሰላምን አመጣለሁና፣ ሕይወትም የእርሱ ነው፣ ገናናነት በፊቱ ነው፣ ለሰላሙም ፍጻሜ የለውም ያለውን አላወቁም

፹፬. ፍጻሜ በሌላት ምግባራቸውም ክፋት ስለዚህም አቤቱ ቃላችንን ማን ያምነናል? ክንድህስ ለማን ተገለጠ? አለ ::

፪. ኢሳ. ፯. ፲፬ - ፲፭
፫. ኢሳ. ፱. ፮ - ፯

፹፭. ወካዕበ ይቤ ሰሚዐ ትሰምዑ ወኢትሌብዉ ወሪእየ ትሬእዩ ወኢተአምሩ እስመ ጽሉል ልቦሙ ለዝንቱ ሕዝብ::

፹፭. ዳግመኛም መስማትን ትሰ ማላችሁ አታስተውሉም፣ ማየትን ታያላችሁ አታውቁም አለ፣ የዚህ ሕዝብ ልቡና የደነቆረ ነውና::

፹፮. ወበእንተዝ ተሠወረት እምኔሆሙ ጥበብ እስመ ርእዮሙ ኢየአምሩ ወሰሚዖሙ ኢይሌብዉ::

፹፮. ስለዚህም ጥበብ ከነርሱ ተሠወረች፣ አይተው አያውቁምና፣ ሰምተውም አያስተውሉምና::

፹፯. ወአንትሙሰ ሕዝብ በከመ ተውህበ መንግሥት እንዘ ቀዲሙ ኢተአምርዎ ለእግዚአብሔር ወይእዜሰ አእመርክምዎ በርትዕት ሃይማኖት ወስብከተ ወንጌል ለኢየሱስ ክርስቶስ መድኃኒነ ወሀቤ ሕይወት ለኵሎሙ እለ ይሴፈዉ ኪያሁ::

፹፯. እናንተ ሕዝቦች ግን መንግሥተ ሰማያት እንደተሰጣችሁ መጠን ቀድሞ እግዚአብሔርን ሳታውቁት ትኖሩ ነበረ፣ ዛሬ ግን በቀናች ሃይማኖት በወንጌል ትምህርት እርሱን ተስፋ ለሚያደርጉ ሰዎች ሁሉ ሕይወትን የሚሰጥ መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስን አወቃችሁት::

፹፰. ናሁ አንትሙሰ ኀደግሙ አምልኮ ጣዖታት እለ አልቦሙ ነፍስ ወመነንክሙ መሥዋዕተ ርኩሰ ወክሕድክምዎሙ ለመኳንንተ ጽልመት::

፹፰. እነሆ እናንተስ ነፍስ የሌላቸው ጣዖታትን ማምለክን ተዋችሁ፣ የጨለማ አበጋዞችን ክዳችሁ ርኩስ መሥዋዕትን ናቃችሁ::

፹፱. ወበእንተዝ ቦእክሙ ውስተ ብርሃን ዘበአማን በእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወቦቱ አእምርክምዎ ለ፩ ጻድቅ እግዚአብሔር አብ፤ ወኮንክሙ ወራስያነ መንግሥቱ ለክርስቶስ እስመ ተጠመቅሙ በሞቱ ወበትንሣኤሁ::

፹፱. ስለዚህም በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ወደ እውነተኛው ብርሃን ገባችሁ፣ በርሱም አንድ እውነተኛ እግዚአብሔር አብን አወቃችሁት፣ የክርስቶስ መንግሥቱንም ወራሾች ሁናችሁ፤ በሞቱ በትንሣኤው ተጠምቃችኋልና::

፺. መፍትው ትኩኑ ከመ ሕፃናት እለ ይእዜ ተወልዱ እለ አልቦሙ እከይ ውስተ ልቦሙ::

፺. በልቡናቸው ክፋት እንደሌላቸው ዛሬ እንደተወለዱ ሕፃናት ትሆኑ ዘንድ አገባብ ነው::



፺፩. አዕትቱ እምኔክሙ ኃጢአተ እስመ ቤዘወክሙ በደሙ ክቡር ከመ ታምልክዎ ለእግዚአብሔር ሕያው::

፺፩. ኃጢአትንም ከናንተ አርቁ፣ ሕያው እግዚአብሔርን ታመልኩት ዘንድ በክበረ ደሙ አድኗችኋልና::

፺፪. ይቤ እግዚአብሔር በውእቱ መዋዕል በእንቲ እስራኤል በኀበ እለ ኢየአምኑ ትትሀየድ እምኔሆሙ መንግሥተ ሰማያት ወትትወሀብ ለሕዝብ እለ ይገብሩ ጽድቀ::

፺፪. እግዚአብሔር ስለ እስራኤል በዚያ ወራት እንዲህ አለ፣ ባላመኑ ሰዎች ዘንድ መንግሥተ ሰማያት ከነርሱ ተለይታ ጽድቅን ለሚሠሩ ሰዎች ትሰጣለች አለ::

፺፫. ወአንትሙሰ ቅንኡ ለገቢረ ፍሬ ጥዑም ጥበብ እስመ ኪያክሙ ፈነወ ትካት ኀበ ዐጸደ ወይን::

፺፫. እናንተ ግን ደስ የሚያሰኝ የዕውቀት ፍሬን ለማድረግ መንፈሳዊ ቅንዓትን ቅኑ፣ እናንተን ቀድሞ ወደ ወይን ቦታ ልኳልና::

፺፬. ወእሙንቱሰ ኢይሰምዕዎሙ እስመ አግዘፉ ልቦሙ::

፺፬. እነርሱ ግን አይሰሟቸውም፣ ልቡናቸውን አደንድነዋልና::

፺፭. ወተንሥኡ ላዕለ ዐቀብተ ወይኑ ለእግዚአብሔር ወአኀዝዎሙ ቦ ዘቀተሉ ወቦ ዘወገሩ በዕብን፣ ወቦ ዘቀተሉ በሰይፍ፣ ወቦ ዘወሠሩ በሞሠርት፣ ወቦ ዘቀተሉ በውስተ ቤተ መቅደስ ::

፺፭. የእግዚአብሔርን ወይን በሚጠብቁ ላይ ተነሣስተው ይዘው የገደሉት አለ፣ በድንጋይ የወገሩት አለ፣ በሰይፍ የገደሉት አለ፣ በመጋዝ የተረተሩት አለ፣ በቤተ መቅደስ ውስጥ የገደሉትም አለ::

፺፮. ወዓዲ ቀተልዎ ለወራሲ ወመነንዎ ለዕብን እንተ መነንዎ ነደቅት ::

፺፮. ዳግመኛም ወራሹን ገደሉት አናጢዎች የናቁት ድንጊያንም ናቁት::

፺፯. ወበእንቲኣክሙ ይቤ ሕዝብ ዘኢየአምር ተቀንየ ሊተ ወበውስተ ምስማዐ ዕዝን ተሰጥዉኒ::

፺፯. ስለናንተም ፈንታ የማያውቀኝ ሕዝብ ተገዛልኝ፣ በጆሮ መስሚያ ውስጥ መለሱልኝ አለ::

## አንቀጽ ፴

በእንተ ከመ መፍትው ንለቡ ክርስቲያን ገቢረ ዕለተ ፋሲካ ወኢንስሐት ገቢረ በካልዕ መዋዕል ዘእንበለ በሰሙን በዘቦቱ ይከውን ፍሥሕ አመ ፲ወ፬ ለሠርቀ ሌሊት::

፩. መፍትው ለክሙ አ ፍቁራን አኃው ዘተሣየጠክሙ በደሙ ክቡር ክርስቶስ ትግበሩ በዓለ ቀድስት ፋሲካ በኵሉ ጥንቃቄ ወልቡና ::

፪. እስመ ይዔሪ መዓልት ወሌሊት አመ ፳ወ፭ ለወርኀ መጋቢት::

፫. ጠይቁ እንከ ሐሳበ እስመ ኢሐመ እግዚእነ በአሐቲ ዓመት ፪ተ ጊዜ፣ ወአንትሙኒ ተዓቀቡ ትግበሩ ተዝካረ ሕማማቲሁ አሐተ ጊዜ በዓመት፤ እስመ በእንቲአነ ሞተ ::

፬. ወኢትኅበሩ ገቢረ በዓል ምስለ አይሁድ አስመ አልቦ ፍቅር ማዕከሌነ ወማዕከሌሆሙ እስመ እሙንቱ ስሕቱ በዕበደ አእምሮ ሐሳብ እንዘ ይመስሎሙ ዘይፌጽሙ::

፭. ወበእንተዝ ኮኑ እሡራነ በዲበ ምድር ወውፁኣነ እምጽድቅ::

## ሠላሳኛ አንቀጽ

ክርስቲያን የፋሲካ በዓል የሚደረግበትን ዕለት ማስተዋል እንደሚገባ ይናገራል፣ በዐሥራ አራተኛው ሌሊት ፋሲካ አራት በሚሆንበት በሰሙነ ሕማማት ነው እንጂ በሌላ ቀን በማድረግ እንዳንስት እናስተውል ዘንድ እንዲገባ ይናገራል::

፩. ክርስቶስ በከበረ ደሙ የዋጃችሁ የተወደዳችሁ ወንድሞች ሆይ! የቅድስት ፋሲካን በዓል በፍጹም መረዳትና ማስተዋል ታደርጉ ዘንድ ለእናንተ አገባብ ነው::

፪. በመጋቢት ወር በ፳፭ኛው ቀን መዓልትና ሌሊት ይተካከላልና::

፫. እንግዲህ ቊጥርን ተረዱ፣ ጌታችን በአንዲት ዓመት ሁለት ጊዜ አልታመመምና፣ እናንተም የሕማማቱን መታሰቢያ በዓመት አንድ ጊዜ ታደርጉ ዘንድ ተጠንቀቁ፣ ስለ እኛ ሙቷልና ::

፬. ከአይሁድም ጋር በዓልን አታድርጉ፣ በእኛና በእነርሱ መካከል ፍቅር የለምና፣ እነርሱ የሚፈጽሙ እየመሰላቸው የቊጥር ዕውቀትን በስንፍና ስተዋል::

፭. ስለዚህም በምድር ላይ የታሠሩ ከጽድቅም የወጡ ሆኑ ::



፮. ወአንትሙሰ ዕቀቡ ሐሳበ ዕለት አመ ፳ወ፭ ለወርኀ መጋቢት በሐሳቦሙ ለዕብራውያን::

፯. ወዕቀቡ ዘንተ ሐሳበ እስከ ፳ወ፩ ለሠርቀ ሌሊት ::

፰. ወዓዲ ኢትስሐቱ ሐሳበ ፍሥሕ ከመ ኢይኩን ቅድመ ሆሣዕና ወኢይኩን ፋሲካ ፪ ጊዜ በአሐቲ ዓመት በኢጠይቆ ሐሳብ፣ ዳዕሙ ይኩን ዕለተ ትንሣኤሁ ቅድስት ለእግዚእነ ወአምላክነ ወመድኃኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ በሰንበተ ክርስቲያን ቅድስት::

፱. ወዓዲ ይኩን ጾመ ቅድስት ፋሲካ እምሰኑይ እስከ ቀዳሚት ሰንበት መሐትወ ፋሲካ::

፲. ወበሰሙነ ሕማማት ኢትብልዑ ወኢምንተኒ ዘእበለ ኅብስት ወጼው ወማይ ::

፲፩. ተዐቀቡ በዝንቱ መዋዕለ አጽዋም እምበሊዐ ሥጋ ወሰትየ ወይን እስመ መዋዕለ ላህ ወኀዘን እማንቱ፤ ወፈድፋደሰ በእሉ ሰዱስ ዕለታት::

፲፪. ወእመሰቦ ዘይክል ጸዊመ ይትገኃሥ ፪ ዕለተ ወእመሰ ኢይክል ይጹም በበሐቲ ዕለት ::

፮. እናንተ ግን በዕብራውያን አቈጣጠር የመጋቢት ወር ሃያ አምስተኛ ቀን ቊጥርን ጠብቁ::

፯. ይህን ቁጥር እስከ ሃያ አንደኛው ሠርቀ ሌሊት ድረስ ጠብቁ::

፰. ዳግመኛም የፍስሕን አቈጣጣር አታሳስቱ፣ ከሆሣዕና አስቀድሞ እንዳይሆን፤ ፋሲካም ቊጥርን ባለመጠንቀቅ በአንድ ዓመት ሁለት ጊዜ እንዳይሆን፣ የጌታችን የአምላካችንና የመድኃኒታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ቅድስት ትንሣኤ በተቀደሰች የክርስቲያን ሰንበት ይሁን እንጂ ::

፱. ዳግመኛም የተቀደሰች የፋሲካ ጾም ከሰኞ እስከ ዋዜማዋ ቀዳሚት ሰንበት (ቀዳም ስዑር ይሁን)::

፲. በሕማማት ሳምንትም በጨው ከተሠራ ቂጣና ከውሀ በቀር ምንም አትብሉ አትጠጡ

፲፩. በዚህ የጾም ወራት ሥጋ ከመብላት ጠጅ ከመጠጣት ተጠበቁ፣ የልቅሶና የኀዘን ቀኖች ናቸውና፣ ይልቁንም እኒህን ስድስቱን ቀኖች::

፲፪. መጾም የሚቻለው ሰው ቢኖር ሁለት ቀን ይታገሥ፣ ባይችል ግን በየአንዳንዲቱ ቀን ይጹም ::

፲፫. ወይትዓቀብ እምገቢረ እኩይ እስመ ይቤ እግዚእነ ኢይክሉ ደቂቀ ለመርዓዊ ጾዊመ አምጣነ ሀሎ ምስሌሆሙ መርዓዊ ወባሕቱ ይመጽእ መዋዕል አመ ይነሥእዎ ለመርዓዊ እምኔሆሙ ውእተ አሚረ ይጾውሙ::[1]

፲፬. እስመ በዝንቱ መዋዕል ሰዱስ ነሥእዎ አይሁድ ለእግዚእነ እምኔነ ወሰቀልዎ ዲበ መስቀል ወኆለቍዎ ምስለ ጊጉያን::

፲፭. ወበእንተዝ ንኤዝዘክሙ ትጹሙ ከመ ገበርነ ንሕነ እምድኅረ ዐርገ ውስተ ሰማይ ወባዕዳነሂ መዋዕለ ይጹሙ ረቡዐ ወዓርበ እስከ ተሱዓት ሰዓት ::

፲፮. ወእመቦ ዘያፈቅር ይጹም እስከ የዐርብ ፀሐይ::

፲፯. ወዕቀቡ ሰዓተ ሌሊት እስከ ይነቁ ዶርሆ ተጋቢእክሙ እንከ ውስተ ቤተ ክርስቲያን በስብሐት ወበጸሎት እንዘ ታነብቡ ኦሪተ ወነቢያተ ወመዝሙረ ዳዊት::

፲፰. ወእምድኅረ አጥመቅሙ አንብቡ ወንጌለ በፍርሀት ወበረዓድ ወመሀርዎሙ ለሕዝብ በቍዔተ ወመድኀኒተ ነፍሶሙ::

፲፫. ክፉ ሥራ ከመሥራትም ይጠበቅ፣ ጌታችን የሙሽራ ሚዜዎች ሙሽራው ከእነርሱ ጋራ ሳለ መጾም አይችሉም፣ ነገር ግን ሙሽራውን ከነርሱ የሚወስዱበት ጊዜ ይመጣል ፣ ያን ጊዜ ይጾማሉ እንጂ ብሏልና::

፲፬. በዚህ በስድስተኛው ቀን አይሁድ ጌታን ከኛ ወሰዱት፣ በመስቀል ላይም ሰቀሉት፣ ከበደለኞችም ጋራ ቈጥረውታልና ::

፲፭. ስለዚህም እኛ እንደሠራነው ትጾሙ ዘንድ እናዛችኋለን፣ ወደ ሰማይ ካረገ በኋላ ሌሎችንም ቀኖች ረቡዕንና ዓርብን እስከ ዘጠኝ ሰዓት ይጹሙ ::

፲፮. ፀሐይ እስኪገባ ሊጾም የሚወድ ሰው ቢኖር ይጹም::

፲፯. ከእንግዲህ በኋላ በቤተ ክርስቲያን ተሰብስባችሁ በምስጋና በጸሎት ኦሪትንና ነቢያትን፣ የዳዊትንም መዝሙር እያነበባችሁ የሌሊቱን ሰዓት ዶሮ እስኪ ጮህ ድረስ ጠብቁ ::

፲፰. ካጠመቃችሁም በኋላ በፍርሃትና በመንቀጥቀጥ ሁናችሁ ወንጌልን አንብቡ፣ ለሕዝቡም የሚጠቅመውንና የነፍሳቸውን መድኃኒት አስተምሯቸው::

፩. ማቴ. ፱ ፡ ፲፭



፲፱. ወሰአልዎ ለእግዚአብሔር ከመ ይትመየጥ እስራኤል ውስተ ንስሓ ወይድኅን እምዕልወት እስመ መኰንን ተሐፅበ እደዊሁ በማይ፣ ወይቤ ንጹሕ አነ እም ደሙ ለዝ ብእሲ ጻድቅ::

፳. ወእስራኤልሰ ከልሑ ወይቤሉ ደሙ ላዕሌነ ወላዕለ ውሉድነ::

፳፩. ወእምዝ ይቤሎሙ ጲላጦስ እስቅሎኑ ለንጉሥክሙ ::

፳፪. ወአውሥኡ ወይቤሉ አልብነ ንጉሥ ዘእንበለ ቄሣር ስቅሎ ስቅሎ፤ እስመ ኵሉ ዘያነግሥ ርእሶ ዐላዌ ነጋሢ ውእቱ::[2]

፳፫. ወአውሥኡ ወይቤሉ እመአሕየውኮ ለዝንቱ ኢኮንከ ዐርኮ ለቄሣር።

፳፬. ወእምዝ ጲላጦስ መኰንን ወሄሮድስ ንጉሥ አዘዙ ይስቅልዎ ከመ ይትፌጸም ዘጽሑፍ ዘይቤ ለምንት አንገለጉ አሕዛብ ወሕዝብኒ ነበቡ ከንቶ ወተንሥኡ ነገሥተ ምድር ወመላእክትኒ ተጋብኡ ምስሌሆሙ ኅቡረ ላዕለ እግዚአብሔር ወላዕለ መሲሑ፣[3] ወካዕበ ይቤ ወገደፉ እኅዋሆሙ ከመ በድን ርኩስ::

፲፱. እስራኤልም ወደ ንስሐ ይመለስና ከክህደት ይድን ዘንድ እግዚአብሔርን ለምኑት፣ ፈራጁ ጲላጦስ እኔ ከዚህ ጻድቅ ሰው ደም ንጹሕ ነኝ ብሎ እጆቹን ታጥቧልና::

፳. እስራኤል ግን ደሙ በኛ ላይና በልጆቻችን ላይ ይሁን ብለው ጮሁ::

፳፩. ከዚህ በኋላ ጲላጦስ ንጉሣችሁን ልስቀለውን አላቸው::

፳፪. እነርሱም ያለ ቄሣር ንጉሥ የለንምና ስቀለው ስቀለው ብለው መለሱ፣ ራሱን ንጉሥ የሚያደርግ ሁሉ የንጉሥ ከዳተኛ ነውና::

፳፫. ይህን ብታድነው የቄሣር ወዳጁ አይደለህም ብለው መለሱ::

፳፬. ከዚህም በኋላ ንጉሥ ሄሮድስና መስፍኑ ጲላጦስ ይሰቅሉት ዘንድ አዘዙ፣ "አሕዛብ ለምን ዶለቱ? ሕዝቡስ ከንቱን ለምን ተናገሩ? የምድር ነገሥታትስ ለምን ተነሡ? አለቆችስ ከእነርሱ ጋራ ለምን ተሰበሰቡ? በእግዚአብሔርና በመሲሑ ላይ ለምን ተሰበሰቡ ? ሁለተኛም ወንድማቸውን እንደ ርኩስ በድን ጣሉ" አለ ተብሎ የተጻፈው ይፈጸም ዘንድ::

፪. ዮሐ. ፲፱ ፡ ፲፪–፲፭
፫. መዝ. ፪. ፩–፪

፳፭. ወእምዝ ሰቀልዎ በዓርብ ወተንሥአ በሣልስት ዕለት፤ ተፈጸመ ዘይቤ መጽሐፍ ተንሥእ እግዚኦ ወኰንና ለምድር እስመ አንተ ትወርስ በኵሉ አሕዛብ::

፳፮. ወዓዲ ይቤ ይእዜ እትነሣእ ይቤ እግዚአብሔር እሬሲ መድኀኒተ ወአግህድ ቦቱ ::[፬]

፳፯. ወካዕበ ይቤ ተንሥእ እግዚኦ በመዓትከ ወተለዐል መልዕልቶሙ ለጸላእትከ[፭] ወዐዲ ይቤ ፍድዮሙ ፍዳሆሙ ላዕለ ርእሶሙ::

፳፰. ወበእንተዝ አንትሙኒ አብኡ ቍርባነክሙ በከመ አዘዝክሙ::

፳፱. እስመ ይቤ ከመዝ ግበሩ ተዝካርየ ጹሙኬ ጾመ በፍሥሓ ወበኀሤት ወግበሩ በዓለ እስመ ተንሥአ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ እሙታን ወአሰፈወነ ትንሣኤሁ::

፴. ወዛቲ ሥርዐት ሕገ ትኩንክሙ ዘለዓለም እስከ ይመጽእ ዳግመ በስብሐት እስመ አይሁድሰ ኢአምኑ ትንሣኤሁ ለመድኀኒነ ወንሕነሰ ክርስቲያን ነአምን ትንሣኤሁ እስመ ኵሎሙ ዘይሴፈዉ ትንሣኤሁ ቅድስተ ይረክቡ ሕይወተ ዘለዓለም::

፳፭. ከዚህ በኋላም ዓርብ ቀን ሰቀሉት፣ ተሰቅሎ በሞተ በሦስተኛው ቀን ተነሣ፣ መጽሐፍ አቤቱ «ተነሥተህ ምድርን ግዛት፣ አንተ አሕዛብን ሁሉ ትወርሳለህና» ያለው ተፈጸመ::

፳፮. ዳግመኛም እግዚአብሔር ዛሬ ተነሥቼ መድኃኒትነትን አደርጋለሁ እገለጽበታለሁም አለ::

፳፯. ሁለተኛም አቤቱ በቍጣህ ተነሥ፣ በጠላቶችህም ላይ ከፍ ከፍ በል አለ፣ ዳግመኛም ፍዳቸውን በራሳቸው ላይ አምጣባቸው አለ::

፳፰. ስለዚህም እናንተ እንዳዘዛችሁ ቍርባናችሁን አስገቡ::

፳፱. መታሰቢያየን አድርጉ ብሏልና፣ ጾምንም በደስታና በሐሤት ጹሙ ፣ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከሙታን ተለይቶ ተንሥቶአልና፣ ትንሣኤውንም ተስፋ አድርጎልናልና፣ በዓልን አድርጉ::

፴. ይህችም ሥርዓት ዳግመኛ በጌትነት እስኪመጣ ድረስ ለዘለዓለሙ ሕግ ትሁናችሁ፣ አይሁድ የመድኃኒታችንን ትንሣኤ አላመኑምና፣ እኛ ክርስቲያኖች ግን ትንሣኤውን እናምናለን፣ ቅድስት ትንሣኤውን የሚያምኑ ሁሉ የዘለዓለም ሕይወትን ያገኛሉና::

፬. መዝ. ፲፩ : ፮
፭. መዝ. ፯ : ፯



፴፩. ግበሩ እንከ በዓለ ሰሙነ ዕለተ እስመ እግዚእነ ቦቱ አስተርአየ ለነ፣ ይቤ ቶማስ ሊተኒ አስተርአየኒ ወአስተፍሥሐኒ ቅንዋተ እደዊሁ ወእገሪሁ ወርግዘተ ገቦሁ ቅድስት[፮] እንዘ ቀዲሙ እናፍቅ ወኢየአምን ትንሣኤሁ አርአየኒ ገሀደ ርግዘተ ገቦሁ ዘየማን::

፴፪. ወበ፰ዓ ዕለት ግበሩ በዓለ እስመ ባቲ ፈጸመ ኵሎ ሥርዓተ ወዐርገ ሰማያተ ኀበ አብ ዘአንሥኦ ወነበረ በየማነ ኀይል ወአግረረ ጸላእቶ ታሕተ እገሪሁ ::

፴፫. ወይመጽእ ዳግመ በስብሐት ወበዐቢይ ክብር ይኰንን ሕያዋነ ወሙታነ ወይፈድዮ ለኵሉ በከመ ምግባሩ::

፴፬. ወናሁ ይሬእይዎ ለፍቁር ወልደ እግዚአብሔር ዘሰቀልዎ አይሁድ[፯] እስመ አይሁድ ጉቡኣን እንዘ ያነብቡ ሰቆቃወ ኤርምያስ ነቢይ ::

፴፭. አመ ፲ ለታስዕ ወርኀ[፰] እስመ ለመንፈሰ ሕይወትነ ኢየሱስ ክርስቶስ ነሥእዎ እምኔነ ወአሕመምዎ::

፴፩. እንግዲህ ስምንት ቀን በዓል አድርጉ፣ ጌታችን ለእኛ ተገልጦአልና፣ ቶማስም አለ ፣ ለእኔ የእጆቹንና የእግሮቹን ችንካሮች የቅድስት ጐኑን መወጋትም አሳየኝ፣ አስቀድሜ እጠራጠርና ትንሣኤውን ሳላምን ሳለሁ የቀኝ ጐኑን መወጋት ገልጦ አሳየኝ፣ ደስም አሰኘኝ::

፴፪. በ፬ርባኛው ቀንም በዓልን አድርጉ ሥርዓትን ሁሉ ፈጽሞባታልና ወደ አስነሣው እግዚአብሔር አብ ወደ ሰማያትም ዓርጓልና ጠላቶቹንም ከእግሮቹ በታች አስገዛለት::

፴፫. ዳግመኛም በሕያዋንና በሙታን ይፈርድ ዘንድ በታላቅ ክብርና ጌትነት ይመጣልና፣ ለሁሉም እንደእየ ሥራው ይከፍለዋል::

፴፬. ያን ጊዜም እነሆ የሰቀሉት አይሁድ የተወደደ የእግዚአብሔርን ልጅ ያዩታል፣ አይሁድም በዘጠንኛው ወር በአሥረኛው ቀን የነቢዩ የኤርምያስን የልቅሶ መጽሐፍ እያነበቡ የተሰበሰቡ ናቸው::

፴፭. የሕይወታችን መገኛ ኢየሱስ ክርስቶስን ከእኛ ወስደው መከራን አጽንተውበታልና ::

፮. ዮሐ. ፳ : ፲፯
፯. ማር. ፲፬ : ፵፬
፰. ሰቆ. ኤር. ፬ : ፳

፴፮. ወዓዲ ያንብቡ ዘጸሐፈ ባሮክ እንዘ ይብል ውእቱ አምላክነ ወአልቦ ባዕድ ዘይትማሰሎ ኪያሁ ወውእቱ ረከበ ለኵሉ ፍኖተ ሕይወት ወወሀቦ ለያዕቆብ ገብሩ ወለእስራኤል ፍቁሩ ወእምድኅረዝ ዲበ ምድር አስተርአየ ወአንሶሰወ ከመ ሰብእ::[፱]

፴፯. ወአንቢቦሙ ዘንተ ይበክዩ ወይላህዉ ላሐ ወከመዝ ይትበሩ እንዘ ይሬእዩ መዝበረ ዘገብረ ናቡከደነፆር እንዘ ያመከንዩ ከመ ጥዩቅ ውእቱ::

፴፰. ወእምድኅረ ዐሡር መዋዕል እምዝ ዐርገ፤ ተፍጻሜተ ጰንጠቆስጤ ግበሩ በዓለ::

፴፱. እስመ በይእቲ ዕለት አመ ሣልስ ሰዓት ፈነወ ለነ ጰራቅሊጦስሃ ኢየሱስ ክርስቶስ ወመልአ ላዕሌነ ኃይሎ ወተናገርነ በሐዲስ ልሳን፣ ከመ ውእቱ ኢየሱስ ክርስቶስ መሲሑ ለእግዚአብሔር ዘቦቱ ሥልጣን ይኰንን ሕያዋነ ወሙታነ::[፲]

፵. ወበእንተዝ ስምዐ ኮነ ሙሴ ወይቤ ከመ እግዚአብሔር አምላክነ ነሢአ እሳተ ወአዝነመ::[፲፩]

፵፩. ወከማሁ ርእዮ ያዕቆብ በአምሳለ ብእሲ ወይቤ ርኢክዎ ለእግዚአብሔር አምላክነ ገጸ በገጽ ወድኅነት ነፍስየ ::[፲፪]

፴፮. ዳግመኛም ባሮክ «እርሱን የሚመስለው ሌላ የለምና አምላካችን ነው፣ እርሱም የሕይወትን መንገድ ሁሉ አገኘ፣ ለአገልጋዩ ያዕቆብ ለወዳጁ እስራኤልም ሰጠው፣ ከዚህም በኋላ በምድር ተገለጠ፣ እንደ ሰውም ተመላለሰ» ሲል የጻፈውን ያነብባሉ::

፴፯. ይህንንም አንብበው ያለቅሳሉ፣ ይንሰቀሰቃሉ፣ ናቡከደነፆርም ያደረገውን ፍራሽ አይተው የተረዳ እንደ ሆነ እያመካኙ እንደዚህ ያደርጋሉ::

፴፰. ከዓረገም በኋላ በአስረኛው ቀን በዓለ ሃምሳ ሲፈጸም በዓልን አድርጉ::

፴፱. በዚች ቀን በሦስት ሰዓት ኢየሱስ ክርስቶስ ጰራቅሊጦስን ልኮልናልና፤ በላያችንም ኃይልን መላ፣ ኢየሱስ ክርስቶስ የእግዚአብሔር ልጅ በሕያዋንና በሙታን ይፈርድ ዘንድ ሥልጣን ያለው እንደሆነ በአዲስ ቋንቋ ተናገርን::

፵. ስለዚህም ነገር ሙሴ ፈጣሪያችን እግዚአብሔር እሳትን አንሥቶ እንዳዘነመ ምስክር ሆኖ ተናገረ::

፵፩. እንደዚሁም ያዕቆብ በሰው አምሳል አየው «እንዲህም አለ ፈጣሪያችን እግዚአብሔርን ፊት ለፊት አየሁት ሰውነቴም ዳነች» ::

፱. ባሮክ ፫ ፡ ፲፰–፴
፲. የሐ. ሥራ ፪ ፡ ፬ ፤ ፲ ፡ ፵፪
፲፩. ዘፍ. ፲፱ ፡ ፳፬
፲፪. ዘፍ. ፴፪ ፡ ፴



፵፪. ወአብርሃምኒ ተወክፎ ከመ ነግድ ወአምነ ከመ ውእቱ እግዚአብሔር፤[፲፫] ዘውእቱ ዘርእዮ ኢያሱ ወልደ ነዌ መኰንነ ላዕለ ሠራዊተ ኃይላተ እግዚአብሔር::

፵፫. ወዓዲ ጽኑዕ ውእቱ በንዋየ ሐቅሉ ወረደ በኢያሪኮ ወእምዝ ሰገደ ሎቱ ኢያሱ ከመ ዘይሰግድ ገብር ለእግዚኡ::[፲፬]

፵፬. ወካዕበ ዝውእቱ ዘአመሮ ሳሙኤል ነቢይ ከመ ውእቱ ክርስቶስ መሢሑ ለእግዚአብሔር[፲፭] ወዓዲ ይሰምይዎ ካህናት ወነገሥት መሲሐ::

፵፭. ወዓዲ ውእቱ ዘአመሮ ዳዊት ወይቤ በፍርሀት ከመ ስብሐተ ፍቁር ጐሥዐ ልብየ ቃለ ሠናየ ወአነ አየድዕ ግብርየ ለንጉሥ ከመ ቀለመ ጸሓፌ ዘጠበጠ ይጽሕፍ ልሳንየ ይሤኒ ላህዩ እምውሉደ እመሕያው::

፵፮. ተክዕወ ሞገስ እምከናፍሪከ በእንተዝ ባረከከ እግዚአብሔር ለዓለም::

፵፯. ቅንት ሰይፈከ ኀያል ውስተ ሐቌከ በስንከ ወበላህይከ አርትዕ ተሠራህ ወንግሥ በእንተ ጽድቅ ወርትዕ ወየዋሃት::

፵፪. አብርሃምም እንደ እንግዳ ተቀበለው እግዚአብሔርም እንደሆነ አመነ፣ ይኸውም በእግዚአብሔር ሠራዊት ላይ አለቃ የሆነ የነዌ ልጅ ኢያሱ ያየው ነው::

፵፫. ዳግምኛም በጦር መሣርያ የጸና ነበር፣ በኢያሪኮም የረዳው ከዚህም በኋላ ኢያሱ ባርያ ለጌታው እንደ ሚሰግድ ሰገደለት::

፵፬. ሁለተኛም ነቢዩ ሳሙኤል የእግዚአብሔር መሲሕ ክርስቶስ እንደ ሆነ ያመለከተው ይህ ነው፣ ዳግመኛም ካህናትና ነገሥታት መሲሕ ነው ይሉታል::

፵፭. ዳግመኛም ዳዊት ያመለከተው አውቆት ነው፤ በፍርሃትም እንደ ወዳጅ ምስጋና እንዲህ አለ፣ ልቡናየ በጎ ነገርን አውጥቶ ተናገረ፣ ግብሬንም ለንጉሥ እነግራለሁ፣ አንደበቴም እንደ አማረ ጸሓፊ ቀለም ይጽፋል፣ መልኩም ከሰው ልጅነት ይልቅ ያምራል::

፵፮. ከከንፈሮችህ ባለሟልነት ፈሰሰ፣ ስለዚህም እግዚአብሔር ለዘለዓለሙ መረቀህ::

፵፯. ኃይለኛ ሆይ በደም ግባትህና በመልክህ ላህይ ሰይፍህን በወገብህ ታጠቅ፤ ስለ ጽድቅና ስለ ቅንነት ስለ የዋህነትም ተከናውነህ ንገሥ::

፲፫. ዘፍ. ፲፰ ፡ ፲–፲፯
፲፬. ኢያ. ፭ ፡ ፲፫–፲፭
[illegible]

፴፰፤ወይመርሐከ ስብሐተ የማንከ፣ አሕፃከ ስሑል ኃያል፣ አሕዛብ ይወድቁ ታሕቴከ፣ ውስተ ልቦሙ ለጸላእተ ንጉሥ፡፡

፴፱፤ መንበርከ እግዚኦ ለዓለመ ዓለም በትረ ጽድቅ ወበትረ መንግሥትከ፣ አፍቀርከ ጽድቀ ወዐመፃ ጸላእከ፡፡

፵፤ በእንተዝ ቀብዐከ እግዚአብሔር አምላክከ ቅብዐ ትፍሥሕት እምእለ ከማከ[፲፮]፡፡

፵፩፤ወበእንተዝ ይቤ ሰሎሞን እግዚአብሔር ፈጠረኒ ቀዳሜ ፍኖቱ ለምግባሩ እምቅድመ ዓለም ሣረረኒ መቅድመ ዘእንበለ ምድረ ይግበር ወዘእንበለ ቀላያተ ይግበር ወዘእንበለ ይፃኡ አንቅዕተ ማያት፡፡

፵፪፤ወዘእንበለ አድባር ይጠዐጥዑ እምቅድመ ኵሉ አውግር ወለደኒ[፲፯] ፡፡

፵፫፤ወዓዲ ይቤ ኢሳይያስ ነቢይ ትወጽእ በትር እምሥርወ ዕሤይ ወየዐርግ ጽጌ እምጕንዱ ወይሠየም መኰንነ አሕዛብ[፲፰]፡፡

፲፮ መዝ ፴፱ : ፩- ፲፯
፲፯ ምሳ. ፲. ፳፪. ፳፭
፲፰ ኢሳ. ፲፩. ፩. ፲

፴፰፤የቀኝህ ጌትነትም ይመራሃል፣ ኃያል ሆይ ጦሮችህ የተሳሉ ናቸው፣ አሕዛብ በበታችህ ይወድቃሉ፣ በንጉሥ ጠላቶች ልብ ውስጥ ፡፡

፴፱፤አቤቱ ዙፋንህ ለዘለዓለም ነው፣የመንግሥትህ ሥልጣን የእውነት ሥልጣን ነውና፣ እውነትን ወደድህ ፤ሐሰትን ግን ጠላህ፡፡

፵፤ስለዚህም እግዚአብሔር አምላክ እንዳንተ ያሉት ምእመናን ከሚቀበሉት ልጅነት የበለጠ ደስ የሚያሰኝ ተዋሕዶን አዋሐደህ፡፡

፵፩፤ስለዚህም ነገር ሰሎሞን እንዲህ አለ፣ እግዚአብሔር ለሥራ መንገድ መጀመሪያ አደረገኝ ፣ ከዓለም አስቀድሞ ምድርን ሳይፈጥር ሠራኝ፣ ጥልቆችንም ሳይሠራ የውሀዎች ምንጮችም ሳይወጡ ከዓለሙ ሁሉ አስቀድሞ ሠራኝ ፡፡

፵፪፤ተራሮች ሳይከናወኑ ከኮረብቶችም አስቀድሞ ወለደኝ፤

፵፫፤ ዳግመኛም ነቢዩ ኢሳይያስ «ብትር ከዕሤይ ሥር ትወጣለች፣ ፍሬም ከግንዱ ይወጣል፣ የአሕዛብ ገዥም ሁኖ ይሾማል»አለ፡፡



፵፬፤ ወካዕበ ይቤ ሰሎሞን ጥበብ ሐነጸት ላቲ ቤተ[፲፱] ፡፡

፵፭፤ወዓዲ ይቤ ዘካርያስ ተፈሥሒ ፈድፋደ ወለተ ጽዮን ወስብኪ ወለተ ኢየሩሳሌም ናሁ ይመጽእ ንጉሥኪ ጻድቅ ወመድኅን ወየዋህ ውእቱ ወይጼዐን ዲበ አድግ ወዲበ ዕዋለ አድግ[፳]፡፡

፵፮፤ ወዓዲ ይቤ ዳንኤል ውእቱ ወልደ እጓለ እመሕያው በጽሐ እስከ ብሉየ መዋዕል[፳፩] ፡፡

፵፯፤ ውእቱኬ እምደብር ዘወረደ ዕብን ዘእንበለ እድ[፳፪] ወንሕነኒ ንዜኑ ወንሰብክ ለክሙ ከመ ውእቱ ቃለ እግዚአብሔር ህልው እምቅድመ ዓለም፡፡

፵፰፤ወዓዲ ዕሩይ ውእቱ ምስሌሁ በኵሉ ግብር እመኑ ቦቱ ከመ ትርከቡ ሕይወተ ዘለዓለም፡፡

፵፱፤ወእመሰ ኢአመንክሞዎ ትረክቡ ኵነኔ ወዘሰ ኢየአምን በወልድ ኢይሬእያ ለሕይወት ዘለዓለም ወመቅሠፍተ እግዚአብሔር ይነብር ላዕሌሁ፡፡

፲፱ ምሳ. ፱. ፩
፳ ዘካር፡ ፱- ፱
፳፩ ዳን. ፯ - ፲፫
፳፪ ዳን . ፪. ፴፱ : ፴፭

፵፬፤ሁለተኛም ሰሎሞን ጥበብ ለራሷ ቤትን ሠራች አለ ፡፡

፵፭፤ዳግመኛም ዘካርያስ የጽዮን ልጅ ሆይ! እጅግ ደስ ይበልሽ፣ የኢየሩሳሌምም ልጅ አዋጅን ንገሪ፣እውነተኛ የሚያድን ኃዳጌ በቀል በአህያ ላይና በውርንጫዋም ላይ ተቀምጦ ንጉሥሽ ይመጣል አለ ፡፡

፵፮፤ዳግመኛም ዳንኤል የሰው ልጅ እርሱ ከዘመን አስቀድሞ የነበረ ዘመንን አሳልፎ የሚኖር ከመሆን ደረሰ አለ ፡፡

፵፯፤ይኸውም የሰው እጅ ሳይፈነቅለው ከተራራ የወረደ ደንጊያ ነው እኛም ከዓለም አስቀድሞ የነበረ የእግዚአብሔር ቃል እንደሆነ ለናንተ እንነግራለን እናስተምራለን ፡፡

፵፰፤ ዳግመኛም ከርሱ ጋራ በሥራው ሁሉ የተካከለ ነው፣ የዘለዓለም ሕይወትን ታገኙ ዘንድ እመኑበት፡፡

፵፱፤ባታምኑበት ግን የዘለዓለም ቅጣትን ታገኛላችሁ፣ በወልድ የማያምን ግን የዘለዓለም ሕይወትን አያያትም፣የእግዚአብሔርም መቅሰፍት በርሱ ላይ ይኖራል፡፡

፳፥ወእምድኅረ በዓለ ሃምሳ ግበሩ በዓለ ሰቡዐ ዕለተ ወእምዝ ጹሙ እስመ መፍትው ለነ ንትፈሣሕ ወንትሐሠይ እስመ ከፈለነ ንን ሣእ ጸጋ መንፈስ ቅዱስ ።

፳፩፥ሙሴሰ ወኤልያስ ጾሙ ፵ ዕለተ፤ ወዳንኤልኒ ጾመ ፫ ሰንበ ታተ ወኢበልዐ እክለ ለፍትወቱ ሥጋኒ ወወይን ኢቦአ ወስተ አፉሁ[፹፫]።

፳፪፥ወብፅዕት ሐና ሶበ ሰአለቶ ለእግዚአብሔር ይጸግዋ ወልደ፣ ሳሙኤልሃ ትቤ ወይነ ኢሰተይኩ ለሰኪር አላ ዳዕሙ ጸንዐ ልብየ በእግዚአብሔር[፹፬] ።

፳፫፥ወሰብአ ነነዌ ጾሙ ፫ መዓልተ ወ፫ ሌሊተ[፹፭] ።

፳፬፥መርዶክዮስ ወአስቴር በጾም ድኅኑ ወዮዲት በጾም ድኅነት እምሆሎፎርኒስ ዕልው[፹፮] ።

፳፭፥ዳዊትኒ ይቤ ደክመ ብረክየ በጾም ወስሕከ ሥጋየ በኀጢአ ቅብዕ[፹፯] ።

፳፮፥ ወአንትሙኒ ጹሙ ወሰአሉ ኀቤሁ ሥርየተ ኃጢአት።

፳፯፥ ወዓዲ ጹሙ ረቡዐ ወዓርበ እንዘ ትመጽዉቱ ለነዳያን፤ ወአክብሩ ሰንበታተ ተጋቢአክሙ በፍሥሓ ወበሐሤት ውስተ ቤተ ክርስቲ ያን።

፹፫ . ዘፀ.፴፬ : ፳፰፥ ዳንኤ.፲- ፪፫
፹፬ . ፩ ሳሙ.፪. ፩
፹፭. ዮና. ፫-፭
፹፮ አስ. ፭. ፹፮ ፵፪
፹፯. መዝ. ፻፰- ፹፬

፳፥ከበዓለ ሃምሳም በኋላ ሰባት ቀን በዓልን አድርጉ፣ ከዚህም ጹሙ፣ ለኛ ፈጽመን ደስ ይለን ዘንድ ይገባናልና፣ የመንፈስ ቅዱስ ሀብትን እንቀበል ዘንድ አድሎናልና።

፳፩፥ሙሴና ኤልያስም ፵ቀን ጾሙ፣ ዳንኤልም ሦስት ሱባዔ ጾመ፣ ለፍላጎቱም እህል አልበ ላም፣ሥጋና ወይንም በአፉ አል ገባም ።

፳፪፥ብፅዕት ሐናም ወንድ ልጅ ሳሙኤልን ይሰጣት ዘንድ እግ ዚአብሔርን በለመነችው ጊዜ ወይ ንን ለመስከር አልጠጣሁም ልቡ ናዬ በእግዚአብሔር ጸና እንጂ አለች።

፳፫፥የነነዌ ሰዎችም ሦስት ቀንና ሦስት ሌሊት ጾሙ ።

፳፬፥መርዶክዮስና አስቴርም በጾም ዳኑ፤ ዮዲትም በጾም ከወንጀለኛ ሆሎፎርኒስ እጅ ዳነች።

፳፭፥ ዳዊትም ጉልበቶቼ በጾም ደከሙ ሥጋየም ቅቤን በማጣት ሻከረ አለ ።

፳፮፥እናንተም ጹሙ የኀጢአትንም ሥርየት ከርሱ ዘንድ ለምኑ ።

፳፯፥ዳግመኛም ለነዳያን እየመጸ ወታችሁ ረቡዕንና ዓርብን ጹሙ፣ በቤተ ክርስቲያንም ተሰብስባችሁ በደስታና በሐሤት ሰንበቶችን አክ ብሩ።



፳፰፥ወባዕዳነሰ ሰንበታተ ኢት ጹሙ ዘእንበለ አሐቲ ዕለት መሐትወ ፋሲካ ።

፳፱፥ወእመሰቦ ዘይጸውም በሰን በተ ክርስቲያን እንተ ይእቲ ትን ሣኤሁ ቅድስት ወጰንጠቆስጤ እስከ በዓለ ፶ ወእለሰ ይገብሩ ከመዝ ወይላህዉ በበዓላተ እግዚ አብሔር አልቦሙ ሥርየተ ኃጢ አቶሙ።

፴፥ ወአንትሙሰ ግበሩ በዓለ መንፈሳዊተ ወግሙራ ኢትረ ስዩ ኀዘነ ውስቴቶን።

## አንቀጽ ፴ወ፩

### በእንተ ፍልጠተ ዕልዋን ወመናፍቃን ኤጲስ ቆጶሳት።

፩፥ቅድመ ተዐቀቡ እምፍልጠተ ዕልዋን ወመናፍቃን ተገኀሡ እምፍኖቶሙ ለርኩሳን ወረኀቁ እምኔሆሙ እስመ ዘይቀርብ ኀቤ ሆሙ ይውዒ በእሳት በላዒ።

፪፥ ኢትሚጡ እንከ ልበክሙ ኀቤሆሙ ወኢትትፈለጡ በበይ ናቲክሙ በአመክንዮ ኑሚአ ሢመት።

፫፥ወእመሰቦ ዘይቀርብ ኀቤሆሙ ወይገብር ምግባሮሙ ይረክብ ኵነኔ ዘለዓለም።

፬፥ለዳታን ወአቤሮን እለ ተቃረ ንዎ ለሙሴ አብቀወት ምድር ወውኅጠቶሙ ወከማሁ ለደቂቀ ቆሬ ፪፻ወ፶ እለ ተቃረንዎ ለአ ሮን በልዓቶሙ እሳት[፩]

፩. ዘኍል ፲፮ - ፴፭

፳፰፥የፋሲካ ዋዜማ ከምትሆን ከአንዲት ቀን በቀር ሌሎች ሰን በታትን ግን አትጹሙ ።

፳፱፥ ቅድስት ትንሣኤው በተደ ረገባት በክርስቲያን ሰ'ንበት እና በጰራቅሊጦስ እስከ በዓለ ሃምሳ የሚጾም ቢኖር፣ እንዲህ ለሚያ ደርጉና በእግዚአብሔር በዓላት ቀን ለሚያዝኑ፣ ለኃጢአታቸው ስርየት የላቸውም።

፴፥እናንተ ግን መንፈሳዊ በዓ ልን አድርጉ፣ በነዚህም ውስጥ ፈጽማችሁ ኃዘንን አታድርጉ ።

## ሠላሳ አንደኛው አንቀጽ

### ከዳተኞችንና የመናፍቃን ኤጲስ ቆጶሳትን ስለመለየት ይናገራል።

፩፥አስቀድማችሁ ከከዳተኞችና ከመ ናፍቃን ስለ መለየት ተጠበቁ፣ ከርኩሳን መንገድ ተለዩ፣ ከእነ ርሱም ራቁ፣ ወደ እነርሱ የሚቀ ርብ በሚባላ እሳት ይቃጠላል ።

፪፥ እንግዲህ ልባችሁን ወደእነ ርሱ አትመልሱ፣ ሹመትን በመ ሻት ምክንያትም እርስ በርሳ ችሁ አትለያዩ።

፫፥ወደ እነርሱ የሚቀርብ ሥራ ቸውንም የሚሠራ ቢኖር የዘለ ዓለም ቅጣት ፍርድን ያገኛል

፬፥ ሙሴን የተቃወሙትን ዳታ ንንና አቤሮንን ምድር ተከፍታ ዋጠቻቸው፤ እንዲሁም አሮ ንን የተቃወሙትን ሁለት መቶ ሃምሳውን የቆሬን ልጆች እሳት በላቻቸው፣የሙሴ እኅት

ወለማርያም እኅተ ሙሴ ሶበ ተዛለፈት ወአውጽዕዋ እምትዕይንት ሰቡዐ ዕለተ እመትቤ እፎ ተዓደወ ሙሴ ወአውሰበ ብእሲተ ነኪርተ[፱]።

፳፮፤ወዓዲ ያዝያን ንጉሠ ይሁዳ አመ ገብረ ግብረ ክህነት ወአዕረገ ዕጣነ ዘኢኮነ መፍትወ ለገቢር፣ እለ አልዓዛር ካህን ወ፹ ካህናት እለ ምስሌሁ ዘለፍዎ ወዐበየ ሰሚዐ ቃሎሙ ወአስተርአየ ውስተ ገጹ ለምጽ እስመ ተምዖ እግዚአብሔር[፲]።

፳፯፤ወእመሰ ነገሥት እምከመ ተዐደዉ ይረክቡ ኵነኔ እፎኬ ፈድፋደ ባዕዳን እለ ይትዐደዉ ላዕለ ካህናት እስመ ክህነት ተዐቢ እመንግሥት።

፳፰፤ካህናትሰ ይቀንዩ ነፍሳተ ወነገሥትኒ ይኴንኑ ሥጋ በመጥባሕት።

፳፱፤ወእለሰ ይትዐደዉ ላዕለ ካህናት ይትኴነኑ ዐቢየ ኵነኔ እምእለ ይትዐደዉ ላዕለ ነገሥት።

፴፤ወባሕቱ አልቦ ዘይክል ድኂነ እምኵነኔ ክልኤሆሙ።

ማርያም ሙሴ እንዴት ተላለፈ ባዕድ ሴትንስ እንዴት አገባ ብላ ባሽሟጠጠች ጊዜ ሰባት ቀን ከከተማ አስወጡአት ።

፳፮፤ዳግመኛም የይሁዳ ንጉሥ ያዝያን ሊያደርገው የማይገባውን የክህነትን ሥራ በሠራና ዕጣን ባሳረገ ጊዜ ካህኑ አልዓዛርና ከእርሱ ጋር የነበሩ ሰማንያ ካህናት መከሩት፣ ቃላቸውን መስማትንም እንቢ አለ፤ በፊቱም ለምጽ ወጣበት፣ እግዚአብሔር ተቆጥቶታልና።

፳፯፤ነገሥታት ሲደፋፈሩ ቅጣትን የሚያገኙ ከሆነ፤ በካህናት ላይ የሚደፋፈሩ ሌሎችማ እንዴታ ክህነት ከመንግሥት ትበልጣለችና።

፳፰፤ካህናት ነፍሳትን ይገዛሉ፣ ነገሥታት ግን ሥጋን በሾተል ይቀጣሉና።

፳፱፤ በካህናት ላይ የሚደፋፈሩ ሰዎች ግን በነገሥት ላይ ከሚደፋፈሩ ሰዎች ይልቅ ታላቅ ቅጣትን ይቀጣሉ ።

፴፤ ነገር ግን ከሁለቱም የቅጣት ፍርድ መዳንን የሚችል የለም።

፱ ዘኁ ፲፪ - ፲፭
፲. ፪ኛ ዜና ፳፮ ፡ ፲፮-፳፪



፲፤ወዓዲ ይቤ በእንተ አቤሴሎም ወደቂቀ ቆሬ ወዳታን ወባዕዳንሂ እለ ይትዓደዉ ክህነተ ኢያድኅኑ ርእሶሙ እምኵነኔ እስመ እሉ ተንሥኡ ላዕለ ዳዊት በእንተ መንግሥት።

፲፩፤ወካዕበ ተቃረንዎ ለሙሴ በአፍቅሮ ከዊነ መኰንን ወአቤሴሎም ረሰየ አባሁ መኰንነ ዐመፃ ።

፲፪፤ወካዕበ ይቤ በእንተ ዳታን ወአቤሮን ወአውሥእዎ ወይቤልዎ ለሙሴ ኢአከለከኑ ዘአውጻእከነ እምብሔረ ግብፅ እምድር እንተ ታውኅዝ ሀሊበ ወመዓረ ወመላህከ አዕይንቲነ ወኮንከ መኰንነ ላዕሌነ[፴] ።

፲፫፤ ወእምዝ ተጋብኡ ብዙኃን ወነብሩ ላዕሌሁ ።

፲፬፤ ወከማሁ ደቂቀ ቆሬኒ ይቤሉ ለሙሴኑ ለባሕቲቱ፣ወለአሮን ሊቀ ካህናት ተናገሮሙ እግዚአብሔር ወበኀበ ደቂቀ እስራኤልሰ አልቦኑ ንጹሕ ዘእንበለ አሮን ባሕቲቱ።

፲፭፤ወበእንተዝ ቦ ዘይቤሉ ለሙሴ መኑ ሤመከ መልአከ ወመኰንነ ላዕሌነ[፳]፤

፴ ዘኁ ፲፮ ፡ ፲፫ - ፲፭
፳ ዘኁል ፲፮ . ፲፫ ፡ዘኁል ፲፪.፪

፲፤ስለ አቤሴሎም፣ ስለ ቆሬ ልጆችና ስለ ዳታን ክህነትንም ስለሚደፋፈሩ ስለ ሌሎችም እንዲህ አለ፣ ራሳቸውን ከቅጣት አያድኑም፣ እነዚህ ስለ መንግሥት በዳዊት ላይ ተነሥተዋልና።

፲፩፤ሁለተኛም ፈራጅ መሆንን በመውደድ ሙሴን ተቃወሙት፣ አቤሴሎምም አባቱን የዓመፃ ገዥ አደረገው ።

፲፪፤ዳግመኛም ስለ ዳታንና አቤሮን እንዲህ አለ፣ ሙሴን ወተትና ማርን ከምታፈስስ ከግብፅ ምድር ያወጣኸን ዐይኖቻችንንም ማውጣትህ በእኛም ላይ አለቃ መሆንህ አልበቃህምን ብለው መለሱለት»

፲፫፤ከዚህ በኋላ ብዙዎች ሰዎች ተሰብስበው በርሱ ላይ ተባበሩ።

፲፬፤እንዲሁም የቆሬ ልጆች እግዚአብሔር ሙሴን ብቻውንና የካህናቱን አለቃ አሮንን ተናገራቸውን በእስራኤል ልጆች ዘንድስ ከአሮን ብቻ በቀር ንጹሕ የለምን አሉ ።

፲፭፤ስለዚህም ሙሴን በእኛ ላይ አለቃና ገዥ አድርጎ ማን ሾመህ ያሉ አሉ።

፲፮፡ ወእምዝ ተንሥኡ ላዕለ ሙሴ ብእሴ እግዚአብሔር ወምእመን ዘገብረ ኵሎ ተአምራተ፣ ወፈጸመ ኵሎ መንክራተ፣ ወአውረደ ላዕለ ሰብአ ግብጽ ብዙኀ መቅሠፍተ፣ ሰጠቀ ማየ ወአቀመ ባሕረ ከመ ዐረፍት እምለፌ፡፡

፲፯፡ ወአውፅኦሙ ለሕዝብ እምህየ ከመ ዘየሐውር ውስተ የብስ ፣ ወተሰጥመ ፈርዖን ወሠራዊቱ ወኵሉ ኀይሉ ውስተ ባሕር፤ ወአንቅዐ ኰኵሐ ወአውሐዘ ሎሙ ማየ፣ ወወሀቦሙ መና እምሰማይ ወአዝነመ ላዕሌሆሙ ሥጋ ከመ መሬት፤ ወመርሖሙ መዓልተ በደመና ወኵሎ ሌሊተ በብርሃነ እሳት[፮]፡፡

፲፰፡ ወዓዲ ወሀቦሙ ሕገ በአፉሁ ለእግዚአብሔር አኃዜ ኵሉ ወ፪ ጽላተ ዘዕብን እለ ጽሑፍ ውስቴቶን ዐሥሩ ቃላት በአፃብዒሁ ለእግዚአብሔር ወተናገሮ እግዚአብሔር ገጸ በገጽ ከመ ይትናገር ብእሲ ምስለ ዐርኩ[፯] ፡፡

፲፮፡ ከዚህ በኋላ የእግዚአብሔር ሰውና ታማኝ በሆነ፣ ታምራቱን ሁሉ በአደረገ፣ ድንቅ ሥራዎችንም ሁሉ በፈጸመ፣ በግብፅ ሰዎችም ላይ ብዙ መቅሠፍትን ባወረደ፣ ውሀንም ከፍሎ በወዲያና በወዲህ እንደ ግድግዳ ባቆመ በሙሴ ላይ ተነሡ፡፡

፲፯፡ ሕዝቡን ከዚያ በደረቅ እንደ ሚሄድ አወጣቸው፣ ፈርዖንም ከሠራዊቱና ከኃያላኑ ሁሉ ጋራ በባሕሩ ውስጥ ተሰጠመ፤ ጭንጫውንም ሠንጥቆ ውሀን አፈሰሰላቸው፣መናንም ከሰማይ ሰጣቸው፤ሥጋንም በላያቸው እንደ መሬት አዘነመ፤ ቀን በደመና ሌሊቱንም በእሳት ብርሃን መራቸው ፡፡

፲፰፡ ዳግመኛም ሁሉን በፈጠረ እግዚአብሔር ቃል ሕግንና በእግዚአብሔር ጣቶች የተጻፉ አሥሩ ቃላት በውስጣቸው የተጻፉባቸው ሁለቱን የደንጊያ ጽላቶች ሰጣቸው፣ እግዚአብሔርም ሰው ከወዳጁ ጋራ እንደ ሚነጋገር ፊት ለፊት ተነጋገረው፡፡

፮ ዘፀ. ፲፮ ፲፫-፲፭፤

፯. ዘፀአ .፴፪.፲፭.፲፮



፲፱፡ ወበእንቲአሁ ይቤ ኢይትነሣእ ነቢይ በከመ ሙሴ [፰] ፡፡

፳፡ ወላዕለ ዝንቱ ብእሲ ተንሥኡ ላዕሌሁ ደቂቀ ቆሬ ወሮቤል ወገርዎ በዕብን እንዘ ይጼሊ[፱]፡፡

፳፩፡ ወውእቱሰ ይብል ኢትነጽር ዲበ መሥዋዕቶሙ ወቍርባኖሙ ወውኅጠቶሙ ምድር ወእምዝ አስተርአየ ስብሐተ እግዚአብሔር፡፡

፳፪፡ ወቦ እለ በልዐቶሙ እሳት ወከማሁ ለእለ የኀሥሡ ሢመተ በዐመፃ ውኅጠቶሙ ምድር ምስለ ተዓይኒሆሙ ወኵሉ ንዋዮሙ ወረዱ ውስተ ሲኦል ሕያዋኒሆሙ[፲]፡፡

፳፫፡ ወእመሰ ለእሉ ፈደዮሙ እግዚአብሔር ኵነኔ መቅሠፍት እፎኬ ላዕለ እለ ይተልዉ ፍኖቶሙ ለዕልዋን ወመናፍቃን ወይፀርፉ ላዕለ ፍጥረተ ግብሩ፡፡

፳፬፡ ወአንትሙኒ ኦ አኃው ስምዑ ቃለ ተግሣጸ መጻሕፍት ወተዐቀቡ እምፍልጠተ አእምሮ ወኢይኩን ሕፁፀ ሃይማኖትክሙ ፡፡

፲፱፡ ስለ እርሱም እንዲህ አለ፣ እንደ ሙሴ ያለ ነቢይ አይነሣም፡፡

፳፡ በዚህ ሰው ላይ የቆሬና የሮቤል ልጆች ተነሥተው እየጸለየ ሳለ በደንጋይ ደበደቡት ፡፡

፳፩፡ እርሱም አለ፣ መሥዋዕታቸውን ቍርባናቸውን አትቀበል፣ ምድርም ዋጠቻቸው፣ ከዚህም በኋላ የእግዚአብሔር ክብር ተገለጠ ፡፡

፳፪፡ እሳት የበላቻቸው አሉ፣ እንዲሁም ሹመትን በዐመፅ ሲፈልጉ ከገንዘባቸው ሁሉና ከከተሞቻቸው ጋራ ምድር የዋጠቻቸው በሕይወታቸውም ሳሉ ወደ ሲኦል የወረዱ አሉ ፡፡

፳፫፡ እግዚአብሔር ለነዚህ የመቅሠፍት ፍርድን ከከፈላቸው የከሐዲዎችንና የመናፍቃንን መንገድ በሚከተሉ ላይና የእጁን ፍጥረት በሚፀርፉ (በሚሰድቡ) ላይማ እንዴት ይሆን?

፳፬፡ ወንድሞች ሆይ፣ እናንተም የመጻሕፍትን ምክር ስሙ ከዕውቀት ከመለየትም ተጠበቁ፣ ሃይማኖታችሁም ጐደሎ አይሁን ፡፡

፰ ዘዳግ ፴፬: ፱

፱ ዘኍ ፲፬ : ፲

፲ ዘኍ ፲፮ : ፴፩

፳፭፤ወኢትኅሥሡ ነሢአ ሢመት በኀበ ዕልዋን ወመናፍቃን እለ ያማስንዎሙ ለሕዝብ።
፳፮፤ረኀቁ እምዕልወቶሙ ወኢ ትትአረክዎሙ እስመ ይቤ እግዚአብሔር ተገኀሡ እምእለ ይገብሩ ከመዝ ከመ ኢትትኀጐሉ ምስሌሆሙ[፲፩]።

፳፯፤መፍትው ተፈልጦ እምእለ ይፀርፉ ላዕለ ስመ እግዚአብሔር እስመ ነቢር ምስለ ዕልዋን ወመናፍቃን ያርኅቅ እምእግዚአብሔር ወእሙንቱ እለ ይትቃረኑ ምስሌሁ ።

፳፰፤ ወበእንተ እከዮሙ ረኵሰት ምድር በከመ ይቤ ኤርምያስ ነቢይ ርኅቁ ዝንቱ ሕዝብ እኩይ እምእግዚአብሔር ሕያው ።

፳፱፤ወካዕበ ይቤ ኀደጉ ቤትየ ወርስትየ ወሜጥኩ ገጽየ እምኔሆሙ።

፴፤ ወካዕበ ይቤ ለዐፀደ ወይንየ ኢይከርይዋ ወኢይገምድዋ ወኢያስተናጽሕዋ አላ ዳዕሙ ይበቊል ውስቴታ ሦክ ወአሜከላ ወኢይኤዝዝ እንከ ዲቤሃ ደመና ከመ ይዝንም ዝናም ወትከውን በድወ[፲፪]

፴፩፤እስመ እግዚአብሔር ኀደጎሙ ለዝንቱ ሕዝብ ከመ ጽላሎተ ሐይመት ማዕከለ ዐጸደ ወይን ወከመ ዐቃቤ ዳስ ወከመ ሀገር ምዝብርት[፲፫]።

፲፩ ዘኍ ፲፮ : ፳፫
፲፪. ኢሳ. ፭ . ፮
፲፫ ኢሳ . ፩ . ፰

፳፭፤ሕዝብን በሚያጠፏቸው በመናፍቃንና በወንጀለኞችም ዘንድ ሹመት መቀበልን አትፈልጉ።
፳፮፤ ከወንጀልኝነታቸው ራቁ፣ ጓደኞችም አትሁኗቸው፣ እግዚአብሔር ከእነርሱ ጋራ እንዳት ጠፉ እንዲህ ከሚያደርጉ ሰዎች ተለዩ ብሏልና።

፳፯፤ በእግዚአብሔር ስም ላይ ከሚሳደቡ ሰዎች መለየት አገባብ ነው፣ ከከሐዲዎችና ከመናፍቃን ጋራ መኖር ከእግዚአብሔር ያርቃልና እነዚህም ከርሱ ጋራ የሚከራከሩ ናቸው ።
፳፰፤ ስለ ክፋታቸውም ምድር ረከሰች፣ ነቢዩ ኤርምያስ ይህ ክፉ ሕዝብ ከሕያው እግዚአብሔር ራቁ እንዳለ ።
፳፱፤ሁለተኛም አለ፣ቤቴንና ርስቴን ተውሁ፣ፊቴንም ከእነርሱ መለስሁ።
፴፤ዳግመኛም አለ፤ የወይን ቦታዬን አይቆፍሯትም፣ አይቆርጧትምም አያፀዷትም፣ነገር ግን በውስጧ እሾህና አሜከላ ይበቅላል፣ እንግዲህም ዝናም ይዘንም ዘንድ ደመናን በእርሷ ላይ አላዝዝም ምድረ በዳም ትሆናለች።
፴፩፤እግዚአብሔር እሊህን ሕዝብ በወይንቦታ መካከል እንዳለ የድንኳን ጥላ እንደ ወይን ጠባቂ ዳስ እንደ ፈረሰችም ከተማ ትቷቸዋልና።



፴፪፤ወአሴሰል እምኔሆሙ መንፈስ ቅዱሰ መንፈሰ ትንቢት።

፴፫፤ ወለዛቲሰ ቤተ ክርስቲያን መልዓ አኰቴተ መንፈሳዊተ ከመ ፈለገ ግብጽ ዘበመዋዕለ ክረምት ወአልዓላ ከመ ቤት ዲበ ርእሰ ደብር ጥሉል[፲፬]።

፴፬፤ደብር ርጉዕ ወደብር ጥሉል ደብር ዘሠምሮ የኀድር እግዚአብሔር ውስቴቱ ወይነብር ለዓለም[፲፭]።

፴፭፤ ወካዕበ ይቤ በኤርምያስ ነቢይ ምግባሩ ለልዑል ስቡሕ ወቅዱስ መካን ድልው ለነ[፲፮]።

፴፮፤ወዓዲ ይቤ በኢሳይያስ በውእቱ መዋዕል ያስተርኢ ደብረ እግዚአብሔር ዲበ አርእስተ አድባር ነዋኃት ወቤተ እግዚአብሔር ላዕለ ማዕዘንት ወይትሌዓል ፈድፋደ መልዕልተ አውግር[፲፯]።

፴፯፤ወበእንተዝ ኀደጎሙ እግዚአብሔር ለሕዝበ አይሁድ ወረሰየ ምኵራቦሙ በድወ ወሠጠጠ መንጦላዕቶሙ ወነሥአ መንፈስ ቅዱሰ እምኔሆሙ በከመ ጽሑፍ ናሁ ይትኀደግ ለክሙ ቤትክሙ በድወ[፲፰] ።

፲፬ ሲራክ ፲፬ : ፳፭
፲፭. መዝ. ፷፯. ፲፮
፲፮ ኤርም ፲፯. ፲፪
፲፯ ኢሳ ፪. ፪
፲፰. ማቴ. ፳፫. ፴፰

፴፪፤ትንቢትን የሚያናግር መንፈስ ቅዱስንም ከእነርሱ አርቃለሁ አለ።
፴፫፤ ይህችን ቤተ ክርስቲያን ግን በክረምት ወራት እንደሚሆን እንደ ግብጽ ፈሳሽ መንፈሳዊ ምስጋናን መላት በለመለመ በተራራ ራስ ላይ እንዳለ ቤትም ከፍ ከፍ አደረጋት።
፴፬፤ የማይናወጽ የለመለመ ተራራ እግዚአብሔር የወደደው በውስጡም እግዚአብሔር አድሮበት ለዘለዓለሙ ይኖራል።
፴፭፤ዳግመኛም ነቢይ ኤርምያስ የልዑል እግዚአብሔር መቀመጫው የተመሰገነ ክቡር ንጹሕ ቦታ ለኛ የተዘጋጀ ነው አለ ።
፴፮፤ዳግመኛም በኢሳይያስ እንዲህ አለ «በዚያ ወራት የእግዚአብሔር ተራራ በረጃጅም ተራሮች ራሶች ላይ፣ የእግዚአብሔርም ቤት በማዕዘኖች ላይ ይታያል፣ በኮረብቶችም ላይ ፈጽሞ ከፍ ከፍ ይላል።»

፴፯፤ስለዚህም እግዚአብሔር የአይሁድ ወገኖችን ተዋቸው፤ ምኵራባቸውንም ምድረ በዳ አደረገ፣ መጋረጃቸውንም ቀደደ፤ ቤታችሁ እነሆ ምድረ በዳን ይሆናል ተብሎ እንደ ተጻፈ መንፈስ ቅዱስን ከነርሱ አራቀ ።

፴፰፤ለክሙስ ሕዝበ ክርስቲያን ተውህበ ለክሙ አኰቴተ መንፈስ ቅዱስ በከመ ጽሑፍ በኢዩኤል ነቢይ እሠውጥ መንፈስየ ዲበ ኵሉ ዘሥጋ ወይትኔበዩ ደቂቅክሙ ወአዋልዲክሙ ወወራዙቲክሙ ራእየ ይሬእዩ ወሊቃውንቲክሙ ሕልመ የሐልሙ[፲፱]:: እስመ ኀይለ ጥበብ ወአእምሮ አሰሰለ እግዚአብሔር እምአይሁድ ወወሀበክሙ ለክሙ::

፴፱፤ ወበእንተዝ ቀንአ ዲያብሎስ ላዕለ ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ዘእግዚአብሔር ወአምጽአ ላዕሌክሙ ፍርሀተ ወረዓደ ሕማመ ወምንዳቤ ወኵሎ ፅርፌተ::

፵፤ ወፍልጠትሰ እምኀበ ዕልዋን እስመ ሰይጣን ቀነዮሙ ለሕዝበ አይሁድ ከመ ይቅትሉ ክርስቶስሃ::

፵፩፤ ወአንትሙሰ ጸላዕክምዎሙ ወመነንክሙ እከየ ምግባሮሙ ወበእንተዝ አምጽአ ላዕሌክሙ መንሱተ ወጽልአ በከመ ገብረ ላዕለ ጻድቅ ኢዮብ[፳]::

፵፪፤ወበከመ ተቃረኖ ለኢያሱ ወልደ ኢዮሴዴቅ[፳፩]:: ወለነኒ ብዙኀ ጊዜ ያተ ይፈቀድ ሰይጣን የሐንፍጸነ ከመ ዐለንስ ወከመ ያድክም ሃይማኖተነ[፳፪]::

፴፰፤ የክርስቲያን ወገኖች ሆይ! ለእናንተ ግን የመንፈስ ቅዱስ ምስጋና ተሰጣችሁ፤ በነቢዩ ኢዩኤል መንፈሴን በሥጋዊ ሁሉ ላይ አሳድራለሁ፤ ወንዶችና ሴቶች ልጆቻችሁም ትንቢትን ይናገራሉ፤ ጐልማሶቻችሁም ራዕይን ያያሉ፤ ሽማግሌዎቻችሁም ሕልምን ያልማሉ፣ ተብሎ እንደ ተጻፈ እግዚአብሔር ጥበብንና ዕውቀትን ከአይሁድ አርቆ ለእናንተ ሰጥቶአችኋልና ::

፴፱፤ስለዚህም ዲያብሎስ በተቀደሰች የእግዚአብሔር ቤተ ክርስቲያን ላይ ቀና በእናንተም ላይ ፍርሃትንና እንቅጥቅጥን፣ ሕማምንና ጭንቅን፣ ጽርፈትንም ሁሉ አመጣባችሁ ::

፵፤ከወንጀለኞች መለየትም ይህ ነው፣ሰይጣን የአይሁድን ሕዝብ ክርስቶስን ይገድሉ ዘንድ ገዝቷቸዋልና::

፵፩፤እናንተ ግን ጠላችኋቸው፣ የሥራቸውንም ክፋት ናቃችሁ ስለዚህም በጻድቅ ኢዮብ ላይ እንዳደረገው ፈተናንና ጠብን በእናንተ ላይ አመጣ ::

፵፪፤ የኢዮሴዴቅ ልጅ ኢያሱንም እንደ ተቃረነው እኛንም ሰይጣን ብዙ ጊዜ እንደ አጃ ያንጠረጥረን፣ ሃይማኖታችንንም ያደክም ዘንድ ይወዳል ::

[፲፱] ኢዩኤል.፪. ፳፱ ፤ የሐ ሥራ ፪. ፲፯
[፳]. ኢዮብ . ፪. ፯
[፳፩]. ዘካ፡ ፫..፩ . ፪
[፳፪]. ሉቃ ፳፪.. ፴.፩



፵፫፤ ወባሕቱ እግዚእነ ይምህረነ ረገሞ ወገሠፆ እንዘ ይብል ለያኀሥርከ እግዚአብሔር ዘአድኀነነ ለእስራኤል እስመ ይቤ ቀዲሙ እንዘ ጉቡኣን አንትሙ ሰአልክዎ ለአብ በእንቲአክሙ ከመ ኢይድክም ሃይማኖትክሙ[፳፫] ::

፵፬፤ እስመ ኮነ ፍልጠት ወኃዕዝ እኩይ ማዕከለ ማኀበረ አይሁድ ወሰዱቃውያን እለ ኢየአምኑ ትንሣኤ ሙታን ወፈሪሳውያን እለ ይብሉ ሶበ ተወልደ ብእሲ ይጸሐፍ ላዕሌሁ ኵሎ ዘይገብር ኀጢአተ::

፵፭፤ወዘሂ ይከውን እሉኬ ኢየአምኑ ግብሮ ለእግዚአብሔር ላዕሌነ ወካዕበ ይብሉ ኢይትነሥኡ ሙታን በአሐቲ ሰዓት::

፵፮፤ወእሙንቱሰ ኢየአምኑ ትንሣኤ ወቦ ዕደው እለ ኢይጥዕሙ እክለ ዘእንበለ ያጥምቁ ኵሎ ጊዜ ዐራታተ ወኵሳኵሳተ ወአጽሕልተ ወጽዋዓተ ወምንባራተ የሐፅቡ ወያነጽሑ በማይ[፳፬]፤

፵፯፤ወቦ ካልኣን እለ ይሰመዩ ፍዮኒዮክን እለ ይኄልዩ ወይብሉ ከመ ወልደ እግዚአብሔር ብእሲ ውእቱ ወተወልደ በፍትወተ ሥጋ በሩካቤ ዮሴፍ ወማርያም እንዘ ንጹሓን እሙንቱ እምዘ ከመዝ ግብር::

፵፫፤ነገር ግን ጌታችን ያስተምረናል፣ እኛን እስራኤልን ያዳነን እግዚአብሔር ያዋርድህ ይገሥጽህ ብሎ ረገመው ገሠፀውም፤ እናንተ ቀድሞ ተሰብስባችሁ ሳላችሁ ሃይማኖታችሁ እንዳይደክም ስለናንተ አብን ለመንኩት ብሏልና ::

፵፬፤በአይሁድ ማኀበር የሙታንን መነሣት በማያምኑ በሰዱቃውያንና ሰው በተወለደ ጊዜ የሚሠራው ኃጢአት ሁሉ የሚሆነውም በእርሱ ላይ ይጻፋል በሚሉ ፈሪሳውያን መካከል ክፉ ክፉ ክርክርና መለያየት ተደርጓልና::

፵፭፤እሊህም በኛ ላይ የእግዚአብሔርን ሥራ አያምኑም፣ ሁለተኛም ሙታን ባንዲት ሰዓት አይነሡም ይላሉ ::

፵፮፤እሊህ ግን የእርሱን ትንሣኤ አያምኑም፣ ሁለጊዜ አልጋዎችንና ቍሳቁሶችን ሳያጠምቁ የፃሕሎችንና ጽዋዎችን መቀመጫዎችንም ሳያጠምቁ በውሃ ሳያጥቡና ሳያጠሩ እህልን የማይቀምሱ አሉ::

፵፯፤ እንደዚህ ካለ ሥራ ንጹሐን ሲሆኑ የእግዚአብሔር አብ ልጅ ወልድ በማርያምና በዮሴፍ ሩካቤ በሥጋ ፈቃድ የተወለደ ሰው ነው ብለው የሚያስቡ ፍዮኒዮክን የሚባሉ ሌሎች መናፍቃንም አሉ ::

[፳፫] ሉቃ. ፳፪. ፴፩. ፴፪
[፳፬]. ማር. ፯. . ፫. ፬

፴፰፤እሉኬ እለ እምትካት የዐቅቡ ሕገ አበዊሆሙ ::

አንቀጽ ፴ወ፪

በእንተ ዘከመ አብአ ሰይጣን ፍልጠተ ወጋዕዘ ውስተ ቤተ ክርስቲያን በከመ ገብረ ቀዲሙ ላዕለ ሕዝበ እስራኤል ::

፩፤ናሁኬ ርእዩ ወለብዉ ኪና ወምግባሮ ለሰይጣን ጸላኤ ኵሉ ሠናያት ዘከመ ይገብር ፍልጠተ ወኑፋቄ ወዕልወተ ማእከለ አሕዛብ::

፪፤ቀዳሚ ፍልጠት ዘገብረ ሞስለ ሲሞን በሀገር እንተ ጎቶን ::

፫፤ ወውእቱስ ብእሲ መሠርይ በኪነ ርእሱ ርኩስ ለብሶ ለሰይጣን ከመ ልብስ ወተቀንየ ሎቱ ከመ ገብር እንዘ ኵሎ እኩየ ፈቃደ ይገብር[፩]::

፬፤ወፊልጶስ ወንጌላዊ እኑነ ገብረ ኀይለ ወተአምራተ ዐበይተ ወፈወሰ ዱያነ በሀገረ ሰማርያ በጸጋ እግዚአብሔር ወበትእምርተ መንፈስ ቅዱስ::

፭፤ወርእዮሙ ሰብአ ሰማርያ ኵሎ ምግባሮ ጸንዑ በሃይማኖቶሙ ወአምኑ በእግዚአብሔር ወተጠምቁ በስመ ኢየሱስ ክርስቶስ ::

፩. ግብ ሐዋ. ፰. ፱ ፲፩

፴፰፤ እሊህም ከቀድሞ ጀምሮ የአባቶቻቸውን ሥርዓት ይጠብቃሉ::

ሠላሳ ሁለተኛ አንቀጽ

ሰይጣን ቀድሞ በእስራኤል ላይ እንዳደረገው በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ክርክርንና መለያየትን እንዳስገባ ይናገራል::

፩፤ እነሆ መለያየትንና ጥርጥርን መወንጀልንም በሕዝብ መካከል እንደሚያደርግ በጐዎች ሥራዎችን ሁሉ የሚጠላ የሰይጣንን ተንኰልና ሥራ እዩ አስተውሉ ::

፪፤ስሟ ጎቶን በምትባል አገር ላይ ከሲሞን ጋራ ያደረገው መለያየት መጀመሪያ ነው ::

፫፤ ይህ ሥራየኛ ሰው በረከሰ በራሱ ተንኰል ሰይጣንን እንደ ልብስ ለበሰው፣ ክፉ ፈቃድንም ሁሉ እየሠራ እንደ ባሪያ ተገዛለት::

፬፤ወንድማችን ወንጌላዊው ፊልጶስም ኀይልንና ታላላቆች ታምራትን አደረገ፣ በእግዚአብሔር ጸጋና በመንፈስ ቅዱስ ምልክትነት በሰማርያ ሀገር ድውያንን ፈወሰ::

፭፤የሰማርያ ሰዎችም ሥራውን ሁሉ አይተው በሃይማኖታቸው ጸኑ፣ በእግዚአብሔርም አመኑ፣ በኢየሱስ ክርስቶስ ስምም ተጠመቁ::



፮፤ወሶበ ርእየ ሲሞን መሠርይ ተአምረ ወመንክረ ዘኢኮነ በኪነ ሥራይ አኀዞ መድምም ወበጊዜሃ አምነ ወተጠምቀ ወእምዝ ጾመ ወጸለየ[፪] ::

፯፤ወሰሚዐነ ዘንተ አእኰትናሁ ለእግዚአብሔር በእንተ ዘአምኑ ሰብአ ሰማርያ በስብከቱ ለፊልጶስ::

፰፤ ወእምዝ ተንሣእነ ወሖርነ ኀቤሆሙ፤ ወመሀርናሆሙ ቃለ ተግሣፅ ጥዩቀ ወለእለ ነሥኡ ጥምቀተ አንበርነ እደ ላዕሌሆሙ ወበጸሎት ሀብተ መንፈስ ቅዱስ ጸገውናሆሙ ::

፱፤ወርእዮ ሲሞን ከመ ኀበ ወደይነ እደዊነ ይወርድ መንፈስ ቅዱስ ለእለ አምኑ መጽአ ኀቤነ ነሢኦ ኅልያነ እንዘ ይብል ሀቡኒ ዘ ሥልጣነ ሊተኒ ከመ ኀበ ወደይኩ እዴየ ይረድ መንፈስ ቅዱስ ላዕሌሆሙ[፫]::

፲፤እስመ ይፈቅድ ሰይጣን አስሕቶ ለእለ ይፈቅዱ አሚነ በከመ አስሐቶ ለአዳም ወበልዐ እምዕፀ ወአውፅኦ እምገነት፤ ወአምጽአ ላዕሌሁ ኵነኔ ሞት፤ ወከማሁ ለነኒ ያሠግረነ ከመ ንንሣእ ኅልያነ ወእ

፪. የሐ.ሥራ. ፰. . ፲፫
፫. የሐ.ሥራ. ፰ ፲፰ . ፲፱

፮፤ ሥራየኛው ሲሞንም በሥራይ ተንኰል ያልሆነ ተአምርንና ድንቅ ነገርን በአየ ጊዜ አድናቆት ያዘው በዚያም ጊዜ አምኖ ተጠመቀ፣ ከዚህም በኋላ ጾመ ጸለየ::

፯፤ ይኸነንም ሰምተን የሰማርያ ሰዎች በፊልጶስ ትምህርት ስለ አመኑ እግዚአብሔርን አመሰገን ነው ::

፰፤ከዚህም ተነሥተን ወደ እነርሱ ሄድን፣ የምክር ቃልንም ፈጽመን አስተማርናቸው፣ ጥምቀትንም በተቀበሉ ላይ እጃችንን ጭነን በጸሎት የመንፈስ ቅዱስን ሀብት ሰጠናቸው ::

፱፤ሲሞንም እጆቻችንን ከጫንበት ዘንድ ላመኑ ሰዎች መንፈስ ቅዱስ እንዲወርድ ባየ ጊዜ መማለጃን ይዞ እጄን ወደ ጫንኩባቸው መንፈስ ቅዱስ በላያቸው ይወርድ ዘንድ ለእኔም ይኸን ሥልጣን ስጡኝ እያለ ወደኛ መጣ ::

፲፤ ሰይጣን አዳምን እንዳሳተው፣ ከዕፀ በለስም በልቶ ከገነት እንዳወጣው፣ የሞት ፍርድንም እንዳመጣበት፣ ሃይማኖትን የሚወዱትን ለማሳት ይፈልጋል፤ እንዲሁ እኛንም መማለጃን

ምክመ ነሣእነ ንክውን ዕሩቃነ እመ ንፈስ ቅዱስ ዘነሣእነ ዘእንበለ ሤጥ ህየንተ ንዋይ ዘይበሊ ወይማስን።

፲፩፡ወእምድኅረዝ ፈራህነ ወደንገፅነ ወርእዩየ አነ ጴጥሮስ ዘንተ እኩየ ምግባረ እቤሎ ለሲሞን ወርቅከ ወብሩርከ ይኩንከ ለህጉል ይመስለከሁ በወርቅ ትሣየጦ ለጸጋ እግዚአብሔር እስመ ኢኮነ ርቱዐ ልብከ በኀበ እግዚአብሔር።

፲፪፡ ተመየጥ እምእከየ ምግባርከ ወሰአል ኀበ እግዚአብሔር ይሥረይ ኃጢአተ ዘሐለየ ልብከ እስመ እሬእየከ ከመ ሕምዝ መሪር አንተ ውስተ ገቢረ ዐመፃ።

፲፫፡ ወእምዝ ፈርሀ ሲሞን ዐቢየ ፍርሀተ ወይቤለኒ ጸልዩ ከመ ኢይብጻሕ ላዕሌየ እምዘ ትቤሉ ዝኩሉ[፱]። ወእምዝ ወፃእነ ንስብክ ውስተ ኵሉ ዓለም ነገረ ሕይወት።

፲፬፡ወሰይጣንሰ ፈነወ ሐዋርያተ ሐሳውያነ ድኅሬነ ወዓዲ አንሥአ እለ ያጸርሩ ስብከተ ወንጌል ወይሬስዩ ሐሰተ ወከንቶ።

፱. የሐሥ ፰. ፲፰. ፳፬.

እንድንቀበል ከተቀበልንም ስለ ሚጠፋው ስለሚበላሸው ገንዘብ ያለዋጋ ከተቀበልነው መንፈስ ቅዱስ የተራቆትን እንድንሆን ያጠምደናል።

፲፩፡ከዚህም በኋላ ፈራን፤ ደነገጥንም እኔ ጴጥሮስም ይህን ክፉ ሥራ አይቼ ሲሞንን እንዲህ አልሁት፣ ልብህ በእግዚአብሔር ዘንድ የቀና አይደለምና የእግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስ ሀብትን በወርቅ የምትገዛው ይመስልሃልን፣ ወርቅና ብርህ ለጥፋት ይሁንህ አልኩት ።

፲፪፡ ከሥራህ ክፋትም ተመለስ፣ ልብህ ያሰበው ኃጢአትን ያስተሠርይልህ ዘንድ ወደ እግዚአብሔር ለምን፣ አንተ በደልን በመሥራት መራራ መርዝ እንደሆንክ አይሃለሁና ።

፲፫፡ከዚህም በኋላ ሲሞን ታላቅ ፍርሃትን ፈራ፣ከምትሉት ከዚህ ሁሉ አንዳች እንዳያደርብኝ ጸልዩልኝ አለን፣ ከዚህም በኋላ የሕይወት ነገር ወንጌልን በዓለሙ ሁሉ እናስተምር ዘንድ ወጣን ።

፲፬፡ሰይጣን ግን ሐሰተኞች ሐዋርያትን በኋላችን ላከ፤ ዳግመኛም የወንጌል ትምህርትን የሚያስተጓጉሉ ሐሰትንና ከንቱንም የሚያደርጉትን አስነሣ።



፲፭፡ወእምዝ ሤሙ አሐደ እምውስቴቶሙ ዘስሙ አክሉናፊስ ወረሰይዎ ምስለ ሲሞን ወእሉ ኮኑ አርድእተ ለእለ ይብልዎ ዶስቴዎስ ወሰዐርዎ እምሢመት ።

፲፮፡ወዓዲ ተማከሩ ምስለ ካልኣን ወገብሩ መካነ ወኀብሩ ውስቴቱ ይግበሩ ዘምሉዕ ጽርፈተ እሉ እሙንቱ ክርንቶስ ማርቆስ ወማናዶሮስ ወባስልድዮስ ወሰርዶሎስ።

፲፯፡ ወዓዲ ቦ ካልኣን እለ ይብሉ ህለዉ ብዙኀን አማልክት።

፲፰፡ባዕዳንሂ እለ ፫ ሢመታት ወካልአን ይትጋብኡ ወይትገዓዙ በበይናቲሆሙ ።

፲፱፡ ወቦ እለ ያመልኩ ብዙኃነ አማልክተ እለ ኢየአምሩ።

፳፡ወቦ ዕደው እለ ይሜህሩ እንዘ ይብሉ ከመ አልቦ ሰብሳብ በኀበ እግዚአብሔር ።

፳፩፡ወቦእለ ይሜንኑ ወያስቈርሩ ትድምርተ ወቦ እለ ይዜምዉ ዘእንበለ ኀፍረት።

፳፪፡ወቦ እለ ይሔስዉ ሕጎ ወመምህሮሙ ቄላይድስ።

፳፫፡ወዓዲ አነ ጴጥሮስ ዘመጽአ ኀቤየ ሲሞን በሀገረ ቂሣርያ ረክብክዎ ለቆርኔሌዎስ ምእመነ በእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ[፳]።

፳. የሐዋ.ሥራ. ፲.፳፬.

፲፭፡ከዚህም በኋላ ከእነርሱ ውስጥ አክሉናፊስ የሚባል አንድ ሰውን ሹመው ከሲሞን ጋራ አደረጉት፣ እነዚህም ዶስቴዎስ ለሚባል ሰው ደቀ መዛሙርት ሁነው ከሹመት ሻሩት ።

፲፮፡ ዳግመኛም ከሌሎች ጋራ ተማከሩ፣ ቦታም ሠሩ፣ ስድብን የተመላ ሥራንም ይሠሩ ዘንድ በውስጡ ተባበሩ፣ እሊኸውም ክርንቶስና ማርቆስ፣ ማናዶሮስና ባስልድዮስ ሰርዶሎስ ናቸው።

፲፯፡ዳግመኛም ብዙዎች ጣዖታት አሉ የሚሉ ሌሎች አሉ ።

፲፰፡ሦስት ሹመት የሚሉ ባዕዳንም አሉ፣ ሌሎችም እየተሰበሰቡ እርስ በእርሳቸው ይከራከራሉ።

፲፱፡የማያውቁ ብዙዎች ጣዖታትን የሚአመልኩም አሉ።

፳፡ጋብቻ በእግዚአብሔር ዘንድ አልታዘዘም እያሉ የሚያስተምሩ ወንዶችም አሉ ።

፳፩፡ሩካቤንም የሚንቁና የሚጸየፉም አሉ ፣ ያለ ኃፍረትም የሚሰስኑ አሉ ።

፳፪፡ ሕጉንም ሐሰት የሚሉ አሉ መምህራቸው ቄላይድስ ነውና።

፳፫፡ዳግመኛም ሲሞን ወደኔ የመጣ እኔ ጴጥሮስ ቆርኔሌዎስን በቂሣርያ ሀገር በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ያመነ ሁኖ አገኘሁት ።

፳፬፤ ወሲሞንስ መሠርይ ያስሕቶሙ ለቡሩካን ወቅዱሳን ውሉድ ዘኬዎስ ዘቀዲሙ መጸብሐዊ ውእቱ ወበርናባስ ወናኪዶስ ወአክላስ እኁሁ ለቀሌምንጦስ ዘተሰይመ ኤጲስ ቆጶስ በሀገረ ሮሜ ዘኮነ ረድአ ለጳውሎስ ጻድቅ በትምህርተ ወንጌል ቅዱስ፡፡

፳፭፤ ወተናገርክዎ ፫ተ ጊዜ ወበነገረ ትንቢት ሞእክዎ በኀይለ እግዚአብሔር፡፡

፳፮፤ወእምዝ ጐየ ወሖረ እስከ ኢጣልያ፤ ወሰበ በጽሐ ሀገረ ሮሜ ሆካ ለቤተ ክርስቲያን ወአማሰነ ሃይማኖቶሙ ለብዙኃን ወአህጕሎሙ ለአሕዛብ ወሜጠሙ ኀቤሁ ወመሀሮሙ ገቢረ ሥራይ ወግብረ ርጕማን አጋንንት ፡፡

፳፯፤ወእምዝ ሖረ ቤተ ርጕማን አማልክቲሆሙ ጊዜ ቀትር ወአንበበ ሎሙ እንዘ ይኔጽር ውስተ ምጽንዓት ወኵሉ ሕዝብ ያንቀዐድዉ ኀቤሁ ፡፡

፳፰፤ወእምዝ ተጽዕነ ላዕለ አጋንንት ወሠረረ ላዕለ ፡፡

፳፬፤ሥራየኛው ሲሞን ግን ቡሩካን ቅዱሳን ልጆችን ቀድሞ ቀራጭ የነበረውን ዘኬዎስንና በርናባስን፤ ናኪዶስንና በሮም ከተማ ኤጲስ ቆጶስነትን የተሾመ በቅዱስ ወንጌል ትምህርት የጻድቁ ጳውሎስ ደቀ መዝሙር የሆነ የቀሌምንጦስ ወንድም አክላስን ያስታቸው ዘንድ ሞከረ ፡፡

፳፭፤ሦስት ጊዜ ተናገርኩት በትንቢት ነገርም በእግዚአብሔር ኃይል አሸነፍኩት ፡፡

፳፮፤ ከዚህም በኋላ ሸሽቶ እስከ አንጦልያ (ኢጣልያ) ሄደ፤ ወደ ሮሜ ከተማም በደረሰ ጊዜ ቤተ ክርስቲያንን አወካት፣ የብዙዎችንም ሃይማኖት አጠፋ፤ አሕዛብንም ወደርሱ መልሶ የተረገሙ የአጋንንትን ሥራና ሥራይ መሥራትን አስተማራቸው ፡፡

፳፯፤ ከዚህም በኋላ በቀትር ጊዜ ወደ ተረገሙ ጣዖቶቻቸው ቤት ሄደ ወደ ሰማይም እየተመለከተ አነበበላቸው ፣ ሕዝቡም ሁሉ ወደ እርሱ አቅንተው ይመለከቱ ነበር፡፡

፳፰፤ከዚህም በኋላ በአጋንንት ላይ ተጭኖ ወደ ላይ ወጣ፡፡



፳፱፤ ወአንሰ ጴጥሮስ ቆምኩ ወጸለይኩ ወርኢኩ እንዘ ይሠርር ላዕለ ምጽንዓት አዐርግ ይብል ውስተ ሰማያት ወያሴፍዎሙ ለሕዝቡ ኵሉ ሠናያተ፡፡

፴፤ወእሙንቱስ የአምንዎ ወይሬስይዎ ከመ አምላክ፡፡

፴፩፤ወአንሰ ሰፋሕኩ እደውየ ወሰአልክዎ ለእግዚአብሔር በኵሉ ልብየ ከመ ያውርዶ ዲበ ምድር ወይቀጥቅጥ ኀይሎሙ ለአጋንንት እለ ያስሕትዎሙ ወያህጕልዎሙ ለሰብእ፡፡

፴፪፤ወካዕበ ሰአልክዎ ለእግዚአብሔር ከመ ኢይቅትሎ አላ ዳዕሙ ከመ ንዋየ ለብሐዊ ይቀጥቅጦ፡፡

፴፫፤ወእምዝ ተመየጥኩ ኀበ ሲሞን ወእቤሎ እመሰ ብእሴ እግዚአብሔር አንተ ወሐዋርያሁ ለኢየሱስ ክርስቶስ ወትሜህር ትእዛዛቲሁ ወጽድቆ ኢትረድ ታሕተ፤ ወእመሰ መስሕት ወማህጕሊ አንተ አ ሲሞን እኤዝዞሙ ለአጋንንት እለ ይጸውሩከ ለከ ለሲሞን መሠርይ፣ ወእብሎሙ ረኀቁ እምኔሁ ወኀድግዎ ይረድ ታሕተ ይኩን ስላቀ በቅድመ እለ አስሐቶሙ ፤

፴፬፤ወሰበ እቤ ከመዝ ጐዩ መናፍስት ርኩሳን ወኀደግዎ ፡፡

፳፱፤እኔም ጴጥሮስ ቆሜ ጸለይሁ፣ ወደ ሰማያት ዐርጋለሁ እያለ ለሕዝቡም መልካሙን ሁሉ ተስፋ እያስደረገ ወደ ጠፈር ሲወጣ አየሁ ፡፡

፴፤እነርሱም ያምኑና እንደ አምላክ ያደርጉት ነበር ፡፡

፴፩፤እኔ ግን እጆቼን ዘርግቼ ወደ ምድር ያወርደውና ሰዎችንም የሚያስቷቸውና የሚያጠፏቸው የአጋንንትን ኃይል ያደክም ዘንድ በፍጹም ልቡናዬ እግዚአብሔርን ለመንሁት ፡፡

፴፪፤ሁለተኛም እንደ ሸክላ ሠሪ ዕቃ ስብርብር ያደርገው ዘንድ ነው እንጂ እንዳይገለው እግዚአብሔርን ለመንሁት፡፡

፴፫፤ ከዚህም በኋላ ወደ ሲሞን ተመልሼ አንተ የእግዚአብሔር ሰው የኢየሱስ ክርስቶስ ሐዋርያው ከሆንህ፣ ትእዛዙንና ጽድቁን የምታስተምርም ከሆንህ፣ ወደ ታች አትውረድ፤ ሲሞን ሆይ! አንተ የምታስትና የምታጠፋ ከሆንህ ግን፣ አንተን ባለሥራዩን ሲሞንን የሚሸከሙህ አጋንንትን «ከእሱ ራቁ፤ ተለዩ፤ ባሳታቸው ሰዎች ፊት መሳለቂያ ይሆን ዘንድ ወደታች እንዲወርድ ተዉት» ብዬ አዝዛቸዋለሁ አልሁት ፡፡

፴፬፤ እንዲህም ባልሁ ጊዜ ርኩሳን መናፍስት ትተውት ሸሹ ፡፡

፴፭፤ወእምዝ ወድቀ ዲበ ምድር ወተቀጥቀጠ በዐቢይ ድንጋፄ ወተሰብረ መለያልዩሁ ።

፴፮፤ ወእምዝ ጸርሑ ኵሎሙ ሕዝብ በዐቢይ ቃል ወይቤሉ አሐዱ ውእቱ እግዚአብሔር አምላከ ጴጥሮስ ዘሰበከ ለነ በጽድቅ ወሶቤሃ ኀደግዎ ሰብአ ለሲሞን ።

፴፯፤ ወእምይእቲ ዕለት ጸንዐ ዕልወት ወፍልጠት ማዕከለ ሲሞናውያን ።

፴፰፤ ወእምዝ ቦአ ሰይጣን ውስተ ልቦሙ ለሐሳውያን ነቢያት ዘአስሐቶሙ ወረሰዮሙ ይንብቡ ቃለ ጽርፈት ላዕለ እግዚአብሔር አኃዜ ኵሉ ከመ ኢኮነ አቡሁ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ።

፴፱፤ ወዓዲ ይቤሉ ኢኮነ ፈጣሬ ዓለም አላ ዳዕሙ ውእቱሰ ኢይትረአይ ወኢይትዐወቅ ወአልቦ ስም ወኢተወልደ ።

፵፤ ወካዕበ ይቤሉ ኢኮነ ውእቱ ዘአውረደ ኦሪተ ወነቢያተ ወኢየአምኑ ትንሣኤ ሙታን ወአልቦ ፍዳ በደኃሪት ዕለት ወነፍስኒ ትገብእ ውስተ ፍጥረታ ወይትፌሥሑ በፍትወት ወይትመየጡ ውስተ እኩይ ልማድ ።

፴፭፤ ከዚህም በኋላ በምድር ላይ ወደቀ በታላቅ ድንጋፄም ተሰባበረ ሰውነቱም ሁሉ እንክትክት አለ።

፴፮፤ከዚህም በኋላ ሕዝቡ ሁሉ በታላቅ ቃል ጮሁ፤ እንዲህም አሉ፣ ጴጥሮስ በእውነት የሰበከልን እግዚአብሔር አምላክ አንድ ነው፤ ያን ጊዜም ሕዝቡ ሲሞንን ተዉት ።

፴፯፤ከዚችም ቀን ጀምሮ በሲሞን ወገኖች መካከል ክሕደትና መለያየት ጸና።

፴፰፤ከዚህም በኋላ ሰይጣን ባሳታቸውና የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ አባት እንዳይደለ ሁሉን በፈጠረ በእግዚአብሔር ላይ የስድብ ቃልን እንዲናገሩ በአደረጋቸው በሐሰተኞች ነቢያት ልብ ገባ ።

፴፱፤ ዳግመኛም አሉ፤ የዓለም ፈጣሪ አይደለም፤ ነገር ግን እርሱ አይታይም፤ አይታወቅ ምም፤ ስም የለውም፤ የተወለደም አይደለም።

፵፤ሁለተኛም ኦሪትንና ነቢያትን ያወረደ እርሱ አይደለም አሉ፤ የሙታንን ትንሣኤም አያምኑም፤ በኋለኛዪቱም ቀን ፍዳ የለም፤ ነፍስም ወደ ቀደመው ተፈጥሮዋ ትመለሳለች፤ ይላሉ፣ በፍትወትም ደስ ይላቸዋል፤ ወደ ክፉ ልማድም ይመለሳሉ ።



፵፩፤ወቦ ባዕዳንሂ እለ ይብሉ ብዙኃን አማልክት ወይብሉ ፫ ሢመታት ወቦ እለ ይቤሉ ፪ ሢመታት።

፵፪፤ወካልኣን ይከልኡ አውስቦ ወይኤዝዙ ኢይስተዩ ወይነ እንዘ ያስተራኵሱ ወይጸልኡ ሰብሳበ ወልደተ ወበሊዐ ፍሬያት ።

፵፫፤ ወያርእዩ ርእሶሙ ከመ ንጹሓን እሙንቱ ወይትዌከፉ እኪተ ጥበበ ወይትሜሰሉ ከመ ጻድቃን ወመሃይምናን ።

፵፬፤ወቦ እምኔሆሙ እለ ይኤዝዙ ከመ ኢይብልዑ ሥጋ እንዘ ይብሉ ለእንሰሳ ቦቱ ንባብ ወነፍስ።

፵፭፤ወዓዲ ይቤሉ ዘይትዐደው ላዕለ እንስሳ ይከውን ከመ ቀታሌ ነፍስ ።

፵፮፤ወቦ እለ ይብሉ ሥጋ አኅርው ንጹሕ፤ ባሕቱ ኢኮነ ንጹሐ አላ ርኩስ።

፵፯፤መፍትው ለነ ንርኀቅ እምዘ ከመዝ ግብር ወዘሰ ኮነ ንጹሐ በውስተ ሕግ ይብልዐ እምኔሁ።

፵፩፤አምላኮች ብዙዎች ናቸው የሚሉ ሌሎችም አሉ፣ ሢመታትም ሦስት ናቸው የሚሉ አሉ፤ ሢመታት ሁለት ናቸው የሚሉም አሉ፤ ሢመታት የሚለውን አማልክት የሚል ዘር ይገኛል «የማይቈጠሩ ኀይላትም አሉ» ብሎ የሚጨምር ዘርም አለ ።

፵፪፤ሌሎችም መጋባትን ይከለክላሉ መጋባትንና ልጅ መውለድን ፍሬዎችን መብላትንም እያራከሱና እያጥላሉ ወይንን እንዳይጠጡ ያዝዛሉ፤

፵፫፤እነርሱም ንጹሐን እንደሆኑ እርሳቸውን ያሳያሉ፣ ክፉ ተንኮልንም ተቀብለው እንደ ጻድቃንና እንደ ምእመናን ይመስላሉ ።

፵፬፤ ከነርሱም ወገን እንስሳ ነፍስና መናገር አለው እያሉ ሥጋን እንዳይበሉ የሚአዝዙ አሉ ።

፵፭፤ ዳግመኛም በእንስሳ ላይ የሚደፋፈር ሰው እንደ ነፍሰ ገዳይ ይሆናል ይላሉ ።

፵፮፤የእሪያዎች ሥጋ ንጹሕ ነው የሚሉ አሉ፣ ነገር ግን ርኩስ ነው እንጂ ንጹሕ አይደለም።

፵፯፤ከእንደዚህ ያለ ሥራ እንርቅ ዘንድ ይገባናል፤ በመጽሐፍ ንጹሕ የሆነውን ግን ከእርሱ ይብሉ ።

፶፰፡ወቦ እለ ይትናገሩ ወየአምኑ ከመ ክርስቶስ ብእሲ ቅዱስ ውእቱ አው ከመ አሐዱ እምነቢያት።

፶፱፡ወቦ እለ ይሜህሩ ዝሙተ ገሀደ ዘእንበለ ኀፍረት ወይገብሩ ሥምረተ ሥጋ ወይከውኑ ፍጹማነ ውስተ ኵሉ ምግባር ርኩስ ።

፷፡እስመ ኮኑ እሙንቱ ከመ አርጋኖን ለማኅበረ ዲያብሎስ ወውሉደ መቅሠፍት ።

## አንቀጽ ፴ወ፫

በእንተ ርትዕት ሃይማኖት ወቅድስት ሥላሴ ዘሰበኩ ለነ ሐዋርያት በጽድቅ።

፩፡ወንሕነሰ ደቂቀ እግዚአብሔር ወውሉደ ሰላም ንሰብክ ዘንተ ቃለ ቅዱሰ ለእለ ይትኤዘዙ በርትዕ።

፪፡ነአምን በአሐዱ አምላክ ገባሬ ኵሉ ፍጥረት አብ ለእግዚእነ ወመድኀኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ እስመ አልቦ ውስተ ህላዌሁ አመክንዮ።

፫፡በከመ አቅደምነ ነገረ አላ ባሕቱ ህልው በኵሉ መዋዕል አልቦቱ ጥንት ወኢተፍጻሜት ።

፬፡ወቦቱ ብርሃን ዘኢይጠፍእ ወአልቦ ዘይክል ቀሪቦቶ ኀቤሁ ።

፶፰፡ክርስቶስ ቅዱስ ሰው እንደ ሆነ፣ ወይም ከነቢያት እንደ አንዱ እንደ ሆነ የሚናገሩና የሚያምኑ አሉ።

፶፱፡ያለ ኀፍረትም ገልጸው ዝሙትን የሚያስተምሩ የሥጋንም ፈቃድ የሚሠሩ በርኩስ ሥራ ሁሉ ፍጹማን የሚሆኑ አሉ ።

፷፡ እነርሱ ለዲያብሎስ ማኅበርነት እንደ በገና ኾነዋልና የመቅሠፍትም ልጆች ናቸውና ።

## ሠላሳ ሦስተኛ አንቀጽ

ሐዋርያት ለእኛ በእውነት ስለ አስተማሩን የቀናች ሃይማኖትና ስለ ቅድስት ሥላሴ ይናገራል።

፩፡እኛም የእግዚአብሔር ልጆችና የሰላምም ልጆች በቅንነት ለሚታዘዙ ሰዎች ይህን ቅዱስ ቃል እናስተምራለን።

፪፡በጌታችንና በመድኃኒታችን በኢየሱስ ክርስቶስ አባት ፍጥረቱን ሁሉ በፈጠረ አንድ አምላክ እናምናለን፣ በባሕርዩ ምክንያት የለውምና ።

፫፡አስቀድሞ እንደ ተናገርነ በዘመኑ ሁሉ ህልው ሆኖ ይኖራል እንጂ ጥንትና ፍጻሜ የለውም።

፬፡የማይጠፋ ብርሃን አለው ወደ ርሱ መቅረብ የሚቻለውም የለም።



፭፡ወኢኮነ ፪ተ ወኢ፫ተ፣ ወኢይትዌሰክ ።

፮፡አላ አሐዱ ውእቱ ባሕቲቱ ዘይነብር ለዓለም እስመ ኢኮነ ስውረ ዘኢይትአመር ዳዕሙ ጥዩቀ አእመርናሁ በኦሪት ወበነቢያት።

፯፡ከመ ውእቱ አኃዜ ኵሉ ወሥሉጥ ላዕለ ኵሉ ፍጥረት ።

፰፡ አሐዱ ውእቱ እግዚአብሔር አብ ለእግዚእነ ወመድኃኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ ዘተወልደ እምቅድመ ይትፈጠር ዓለም ወልድ ዋሕድ ዘዕሩይ ምስሌሁ።

፱፡ ገባሬ ኵሉ ሠራዊት፣ ወሢመታት፡ወሥልጣናት ዘሠምረ ይኩን ሰብአ በደኃሪ መዋዕል።

፲፡ወነሥአ ሥጋ እማርያም እምቅድስት ድንግል ዘእንበለ ዘርዐ ብእሲ ።

፲፩፡ወተሐፅነ ከመ ሰብእ ዘእንበለ ኀጢአት ወአበሳ ወአልቦ ጉሕሉት **ውስተ አፉሁ ።**

፲፪፡ወእምዝ ሐመ ወሞተ ዘእንበለ ኀጢአት በሥጋ ወተንሥአ እሙታን በሣልስት ዕለት፡ ወዐርገ ሰማያተ በዐቢይ ሰብሐት ኀበ አብ ዘፈነዎ።

፭፡ሁለት አይደለም በሦስትነቱም አራተኛ አይጨመርበትም ።

፮፡ብቻውን ለዘለዓለሙ የሚኖር አንድ ነው እንጂ የማይታወቅ የተሠወረ አይደለምና በኦሪትና በነቢያት ፈጽመን ዐወቅ ነው እንጂ።

፯፡ሁሉን የያዘ እንደሆነ በፍጥረቱም ሁሉ ላይ የሠለጠነ እንደ ሆነ ።

፰፡ የጌታችን የመድኃኒታችን የኢየሱስ ክርስቶስ አባት እግዚአብሔር አብ አንድ ነው፣ ዓለም ሳይፈጠር የተወለደ አንድያ ልጁ ከእርሱ ጋራ ትክክል የሚሆን።

፱፡ ሠራዊቱን ሁሉና ሢመታትን ሥልጣናትንም የፈጠረ በኋለኛውም ዘመን ሰው ይሆን ዘንድ የወደደ።

፲፡ ያለዘርዐ ብእሲ ክብርት ከምትሆን ከድንግል ማርያም ሥጋን ነሣ።

፲፩፡ያለ ኀጢአትና በደል እንደ ሰው አደገ፣ በአፉም ሽንገላ የለ**በትም።**

፲፪፡ከዚህም በኋላ ያለ በደል በሥጋ መከራን ተቀበለ፣ ሞተ፣ በሶስተኛውም ቀን ከሙታን ተለይቶ ተነሣ፣ በታላቅ ክብርም ወደ ሰማያት ወደላከው ወደ አብ ዐረገ ።

፲፫፡ወነበረ በየማነ ኃይል ወፈነወ ለነ ጰራቅሊጦስሃ መንፈሰ ቅዱሰ ዘወፅአ እምኀበ አብ፡ወአድኀነ ዓለመ ዘሀልው ምስለ አብ ወወልድ።

፲፬፡ንብል እንከ ከመ ኵሉ ሠናይ ፍጥረተ እግዚአብሔር ወአልቦ ግዱፍ ።

፲፭፡ወመንፈስሰ ሕይወተ ሥጋ ይእቲ ንጽሕት ወቅድስት በኵሉ።

፲፮፡ንሕነሰ ንብል ከመ ሰብሳብ ንጹሕ፤ ወልደት አልቦ ርኩስ፤ እስመ ፈጠሮሙ እግዚአብሔር ለአዳም ወለሔዋን ከመ ይብዝኁ ሕዝብ።

፲፯፡ነለቡ እንከ ከመ ቦ ውስተ ሥጋነ ነፍስ እንተ ኢትመውት ወኢትማስን ምስለ ሥጋ።

፲፰፡ንሕነሰ ናስቄርር ኵሎ ግብሮሙ ለዕልዋነ ሃይማኖት ወኵሎ ፍልጠተ ወዐሊወ ሕግ እስመ ርኩሳን እሙንቱ በኀቤነ ።

፲፱፡ ወካዕበ ነአምን ትንሣኤ ሙታን ወከመ ይትነሥኡ ጻድቃን ወኃጥአን ።

፳፡ወበዕለተ ኵነኔ ከመ ይትፈደይ ኵሉ በከመ ምግባሩ።

፲፫፡ኀይል ባለውም ዕሪና ኖረ፤ ከአብ የሠረፀ የሁላችንም መጽናኛ የሚሆን ዓለሙንም ሁሉ ያዳነ ከአብና ከወልድ ጋራ ህልው የሚሆን መንፈስ ቅዱስን ላከልን።

፲፬፡እንግዲህ የእግዚአብሔር ፍጥረት ሁሉ መልካም እንደ ሆነ እንናገራለን የሚጣል የለም፤

፲፭፡የሥጋ ሕይወት የምትሆን ነፍስ ግን በሁሉ ንጽሕትና ክብርት ናት ።

፲፮፡ እኛስ ጋብቻ ንጹሕ እንደ ሆነ ልደትም ርኵሰት እደሌለበት እንናገራለን፤ ሕዝቡ ይበዙ ዘንድ እግዚአብሔር አዳምንና ሔዋንን ፈጥሯቸዋልና ።

፲፯፡እንግዲህ ከሥጋ ጋራ የማትፈርስ፤ የማትበሰብስ ነፍስ በሥጋችን እንዳለች እንወቅ ።

፲፰፡እኛስ ሃይማኖትን የሚክዱትን ሥራቸውን እንጸየፋለን፤ መለየታቸውንም ሁሉ፤ ሕግ መለወጣቸውንም፤እነርሱ በእኛ ዘንድ ርኩሳን ናቸውና።

፲፱፡ዳግመኛም ትንሣኤ ሙታንን እናምናለን፤ ጻድቃንና ኃጥአንም እንደሚነሡ።

፳፡በዕለተ ምጽአትም ሁሉ እንደየሥራው [illegible]



፳፩፡ ወዓዲ ነአምን ከመ ክርስቶስ ኢኮነ ሕፁፀ እምትስብእት ወኢምንትኒ አላ ውእቱ እግዚአብሔር ቃል ዘኮነ ሰብአ በጽድቅ።

፳፪፡ወዐረቀ ትዝምደ ሰብእ ምስለ እግዚአብሔር ሊቀ ካህናቲሁ ለአብ፤

፳፫፡ኢንትገዘር እንከ ከመ አይሁድ እስመ ነአምር ከመ መጽአ ዘይፌጽም ኦሪተ፤ ወነቢያተ።

፳፬፡ዘኪያሁ ይሴፈዉ ምጽአቶ ኵሎሙ አሕዛብ ኢየሱስ ክርስቶስ ዘሠረፀ እምይሁዳ ወእምሥርወ ዕሤይ።

፳፭፡ዘሥልጣኑ ዲበ መትከፍቱ።

፳፮፡እስመ በውእቱ መዋዕል ጸንዐ ዕልወት፤ ወአስሐትዎሙ ለብዙኃን፤ ወበእንተዝ ተሐውከት ቤተ ክርስቲያን ።

፳፯፡ ወእምዝ ተጋባእነ በኢየሩሳሌም ንሕነ እሙንቱ ሐዋርያት፤ ወሜምነ ማትያስሃ ህየንተ ይሁዳ አስቆሮታዊ ።

፳፰፡በከመ ጽሑፍ፤ ወሢመቶሂ ይንሣእ ባዕድ።[፩]

፳፱፡ ወአንገለግነ ምስለ ያዕቆብ እኁሁ ለእግዚእነ ኤጲስ ቆጶስ ዘኢየሩሳሌም ወኀበርነ ምስለ ቀሲሳን ከመ ንንግሮሙ ለአሕዛብ ቃለ ተግሣጽ።

፳፩፡ዳግመኛም ክርስቶስ ሰው ከመሆኑ የተነሣ ምንም ሕጸጽ እንደሌለበት እናምናለን፤ በእውነት ሰው የሆነ የእግዚአብሔር ቃል ነው እንጂ ።

፳፪፡ከአብ ጋራ አስታራቂያችን የሚሆን እርሱ ሰውን ከእግዚአብሔር ጋራ አስታረቀ።

፳፫፡እንግዲህ እንደ አይሁድ አንገዘር፤ ኦሪትንና ነቢያትን የሚያሳልፋቸው እንደ መጣ እናውቃለንና።

፳፬፡አሕዛብ ሁሉ የእርሱን መምጣት ተስፋ የሚያደርጉት ከይሁዳና ከዕሤይ ወገን የተወለደ ኢየሱስ ክርስቶስ።

፳፭፡ሥልጣኑ በጫንቃው የሚሆን።

፳፮፡በዚያ ወራት ክህደት ጸንቷልና ፤ ብዙዎችንም አሳቷቸው፤ ስለዚህም ቤተ ክርስቲያን ታወከች።

፳፯፡ከዚህም በኋላ እኛ ሐዋርያት በኢየሩሳሌም ተሰብስበን ስለ አስቆሮታዊው ይሁዳ ፈንታ ማትያስን ሾምነው።

፳፰፡ሹመቱንም ሌላ ይውሰድ ተብሎ እንደተጻፈ ።

፳፱፡የኢየሩሳሌም ኤጲስ ቆጶስ ከሚሆን ከጌታ ወንድም ከያዕቆብ ጋራ ተሰበሰብን፤ ለሕዝቡም የምክርን ቃል እንነግራቸው ዘንድ ከቀሳውስት ጋራ ተባበርን ።

፩ [illegible]

፴፤እስመ ቦ እለ ወፅኡ እምይሁዳ ወሖሩ አንጾኪያ ይገሥጽዎሙ ለአኃው እለ ውስተ ውእቱ መካን እንዘ ይብሉ እመ ኢተገዘርክሙ በሕገ ሙሴ፤ ወኢሖርክሙ በሥርዐቱ ኢትድኀኑ::

፴፩፤ወኮነ ጋዕዝ፣ ወቀትል::

፴፪፤ወእምዝ አእመሩ አኃው እለ ሀለዉ አንጾኪያ ከመ ተጋባእነ ወኀሠሥነ በእንተ ግብር::

፴፫፤ ወፈነውነ እምኀቤነ ዕደወ መሃይምናነ እለ የአምሩ መጻሕፍተ ቅዱሳተ ያጠይቁ ዘንተ ነገረ::

፴፬፤ ወእሙንቱሰ ወፅኡ ኀቤነ ኢየሩሳሌም ይንግሩነ ኵሎ ዘኮነ በቤተ ክርስቲያን ዘአንጾኪያ ::

፴፭፤ ወቦ እለ ይቤልዎሙ ዕደው መፍትው ትትገዘሩ ወትግበሩ ዘውስተ ሕገ ኦሪት::

፴፮፤ ወአንሰ ጴጥሮስ ተንሣእኩ ወእቤሎሙ ለሕዝብ ኦአኃው ተአምሩ ከመ ኀረዮሙ እግዚአብሔር ለሕዝብ እለ የዐቅቡ ስብከተ ወንጌል ወየአምኑ ለእለ ስምዐ ኮነሎሙ እግዚአብሔር ማእምረ ልብ፤

፴፯፤ ወለቆርኔሌዎስ መኰንነ ምዕት አስተርአዮ መልአከ እግዚአብሔር ፡ ወይቤሎ ጸሎትከ ወምጽዋትከ ዐርገ ቅድመ እግዚአብሔር ተዘካረ ሠናየ::

፴፤ በሙሴ ሕግ ካልተገረዛችሁ በሥርዓቱም ካልሄዳችሁ አትድኑም እያሉ በዚያ ቦታ ያሉትን ወንድሞቻችንን ይገሥጿቸው ዘንድ ከይሁዳ ወጥተው ወደ አንጾኪያ የሔዱ አሉና::

፴፩፤ የሞት ሰልፍና ክርክርም ተደረገ ::

፴፪፤ ከዚህም በኋላ በአንጾኪያ ያሉ ወንድሞቻችን ተሰብስበን የሥራን ነገር እንደ መረመርን አወቁ::

፴፫፤ከእኛም ዘንድ ቅዱሳት መጻሕፍትን የሚያውቁ አማኞችን ይህን ነገር ያስረዱ ዘንድ ላክን ::

፴፬፤እነርሱም በአንጾኪያ ቤተ ክርስቲያን የተደረገውን ሁሉ ይነግሩን ዘንድ፤ እኛ ወደ አለንበት ኢየሩሳሌም ወጡ::

፴፭፤ትገዘሩ በኦሪትም ሕግ ውስጥ ያለውን ትሠሩ ዘንድ አገባብ ነው ያሏቸው ሰዎች አሉ ::

፴፮፤እኔ ጴጥሮስ ግን ተነሥቼ ሕዝቡን ወንድሞቼ ሆይ! የወንጌል ትምህርትን ለሚጠብቁና ለሚያምኑ ልቡናን የሚያውቅ እግዚአብሔር ምስክር እንደሆናቸውና እንደ መረጣቸው ታውቃላችሁ አልኳቸው ::

፴፯፤የመቶ አለቃ ቆርኔሌዎስን የእግዚአብሔር መልአክ ታየው እንዲህም አለው፣ጸሎትህ ምጽዋትህም መልካም መታሰቢያ ሆኖ ወደ እግዚአብሔር ገባ ኋል::



፴፰፤ወይእዜኒ ፈኑ ዕደወ ሀገረ ኢዮጴ ይጸውዕዎ ለከ ለስምዖን ጴጥሮስ ዘየኀድር ቤተ ስምዖን ሰፋዪ ዘመንገለ ባሕር ወውእቱ ይነግረከ በዘተሐዩ አንተ ወኵሉ ቤትከ::

፴፱፤ወኃሊፎ መልአክ ዘተናገሮ ጸውዐ ክልኤተ እምወአልያኒሁ ወአሐደ ሐራ ኄረ እምፀማዱ ወነገሮሙ ኵሎ ወለአኮሙ ሀገረ ኢዮጴ::

፵፤ወእምቅድመ እምጻእ ኀቤሁ ቆምኩ ውስተ ልዑል መካን ወጸለይኩ ጸሎተ ::

፵፩፤ ወናሁ ርኢኩ ተርኅወ ሰማይ ወወረደ ሞጣሕት ዐቢይ ውስተ ምድር ወእኁዝ በጽነፊሁ ::

፵፪፤ወቦ ውስቴቱ አራዊት ወእንስሳ ወአዕዋፈ ሰማይ::

፵፫፤ወሰማዕኩ ቃለ ዘይብል ተንሥእ ጴጥሮስ ኅርድ ወብላዕ ወእቤ ግሙራ ኢቦአ ውስተ አፉየ ርኩስ ዘኢኮነ ንጹሐ::

፵፬፤ ወካዕበ መጽአ ቃል ዘይብል ዘእግዚአብሔር አንጽሖ አንተ ኢታስተራኵስ ወተሰውጠ ኵሉ ውስተ ሰማይ ::

፵፭፤ወእንዘ ከመዝ እሔሊ ምንት ውእቱ ዘአስተርአየኒ ይቤለኒ መንፈስ ቅዱስ ናሁ የኀሥሡከ ዕደው ተንሥእ ወሑር ምስሌሆሙ እንዘ [illegible]

፴፰፤አሁንም ወደ ኢዮጴ ከተማ ሰዎችን ላክ በባሕር አቅራቢያ ባለችው በጫማ ሰፊው በስምዖን ቤት የሚኖረውን ጴጥሮስ የተባለ ስምዖንን ይጥሩልህ፣ እርሱ አንተ ከነቤተሰቦችህ የምትድንበትን ይነግርሃል::

፴፱፤ያነጋገረውም መልአክ ከሔደ በኋላ ከሎሌዎቹ ሁለት፣ ከሚከተሉት አንድ ደግ ወታደር ጠራ፣ ሁሉንም ነግሮ ወደ ኢዮጴ ከተማ ላካቸው::

፵፤ወደ እርሱ ሳልመጣም ከፍ ባለ ቦታ ቁሜ ጸሎትን አደረግሁ::

፵፩፤ወዲያውም ሰማይ ተከፍቶ ዳርና ዳሩ የተያዘ ትልቅ መጋረጃ ከሰማይ ሲወርድ አየሁ ::

፵፪፤በውስጡም አራዊት እንስሳት የሰማይ ወፎችም አሉ::

፵፫፤ጴጥሮስ ሆይ፣ ተነሥተህ አርደህ ብላ የሚል ቃል ሰማሁ፣ ንጹሕ ያልሆነ ርኩስ ፈጽሞ ከአፌ አልገባም አልኩ::

፵፬፤ሁለተኛም እግዚአብሔር ንጹሕ ያደረገውን አንተ አታረካክስ የሚል ቃል መጣ፣ ሁሉም ወደ ሰማይ ተመለሱ ::

፵፭፤የታየኝ ምንድር ነው እያልኩ እንደዚህ ሳስብ መንፈስ ቅዱስ እነሆ ሰዎች ይፈልጉሃል ሳትጠራጠር ተንሥተህ ከነሱ ጋራ ሒድ አለኝ::

፺፮፤ እስመ አነ ፈነውኩ ኀቤከ እሉ እሙንቱ እለ ፈነዎሙ መኰንነ ፪ት፡፡

፺፯፤ወእምዝ ሐለይኩ በልብየ ወአ እመርኩ ቃለ እግዚአብሔር ከመ ውእቱ ተናገረ ወይቤ«ይትፌሥሑ አሕዛብ ምስለ ሕዝቢሆሙ»፤

፺፰፤ወካዕበ ይቤ ይዝክሩ ወይት መየጡ ኀበ እግዚአብሔር ኵሎሙ አጽናፈ ምድር ወይስግዱ ቅድሜሁ ኵሎሙ በሐውርተ አሕዛብ እስመ ለእግዚአብሔር መንግሥት ወውእቱ ይኴንኖሙ ለአሕዛብ[፪]፡፡

፺፱፤ ወዓዲ ተዘከርኩ ዘጽሑፍ በውስተ ጽዋዔ አሕዛብ ወሖርኩ ምስሌሆሙ ወቦእኩ ቤቶ ለውእቱ ብእሲ ወሰበኩ ቃለ ፡፡

፻፤ወሶቤሃ ወረደ መንፈስ ቅዱስ ላዕሌሁ ወዲበ ኵሎሙ እለ ሀለዉ ምስሌሁ በከመ ወረደ ላዕሌነ ወኢ ኮነ ፍልጠት ማዕከሌነ በአሚን ወአ ንጽሐ አልባቢነ ወአእመርኩ ከመ ኢያደሉ እግዚአብሔር ለገጽ፡፡

፻፩፤ወባሕቱ ኵሎሙ አሕዛብ እለ ይፈርህዎ ለእግዚአብሔር ወይገ ብሩ ጽድቀ ይከውኑ ሥሙራነ በኀ ቤሁ፡፡

፪ መዝ ፳፩ ፡ ፳፯ እና ፳፰

፺፮፤እኔ ወደ አንተ ልኬአቸ ዋለሁና እኒህም ሰዎች የመቶ አለቃው የላካቸው ናቸው፡፡

፺፯፤ከዚህ በኋላም በልቤ አሰ ብሁ ሕዝቡም ከወገናቸው ጋር ደስ ይላቸዋል ብሎ እርሱ እን ደተናገረ የእግዚአብሔርንም ቃል አወቅሁ፡፡

፺፰፤ሁለተኛም አለ የምድር ዳር ቻዎች ሁሉ ያስቡ፣ ወደ እግዚ አብሔርም ይመለሱ፣ የአሕዛብ አገሮችም ሁሉ በፊቱ ይስገዱ፣ መንግሥት ለእግዚአብሔር ናትና እሱም አሕዛብን ይገዛቸ ዋልና አለ ፡፡

፺፱፤ዳግመኛም የተጻፈውን የአ ሕዛብን አጠራር አሰብሁ፣ ከነሱ ጋርም ሄድኩ፣ ከዚያም ሰው ቤት ገብቼ ቃሉን አስተማርኩ፡፡

፻፤ ያን ጊዜም በእርሱና ከእ ርሱ ጋር ባሉ ሰዎች ላይ መን ፈስ ቅዱስ ወረደ፣ቀድሞ በእኛ ላይ እንደ ወረደ፣ በኛ መካከ ልም በሃይማኖት መለያየት አል ተደረገም፣ ልቡናችንንም አነጻ፣ እግዚአብሔርም ፊት አይቶ እንዳያዳላ አወቅሁ ፡፡

፻፩፤ነገር ግን እግዚአብሔርን የሚፈሩት ጽድቅንም የሚያደ ርጉ አሕዛብ ሁሉ በእርሱ ዘንድ የተወደዱ ይሆናሉ ፡፡



፻፪፤ወእምዝ ተንሥኡ ላዕሌሁ መሃ ይምናን ወይቤሉ እስከ ማዕዜኑ ታሜክርዎ ለእግዚአብሔር ወታሰ ክምዎሙ ለአሕዛብ ፆረ ክቡደ ዘኢ ይክሉ ፀዊረ ፡፡

፻፫፤ወባሕቱ ንሕነሰ ነአምን ከመ ንድኀን በጸጋ እግዚአብሔር ከማሁ ፈትሐነ እግዚአብሔር እማእሠረ ኃጢ አት ወአቅለለ እምላዕሌነ ጾረ ክቡደ፡፡

፻፬፤ወሶበ ይቤ ከመዝ አርመሙ ኵሎሙ ሕዝብ፡፡

፻፭፤ ወእምዝ አውሥአ ያዕቆብ እኁሁ ለእግዚእነ ወይቤሎሙ ስምዑ ዘእቤለክሙ ናሁ ስምዖን ተና ገረ ቀዲሙ ከመ ኀረየ እግዚአብ ሔር ሕዝበ ለሥርዓቱ ፡፡

፻፮፤በከመ ይቤ መጽሐፍ እመጽእ ወአሐንፅ ቤቶ ለዳዊት ዘተመ ዝበረ ወአነሥኦሙ ለእለ ወድቁ ከመ ይትመየጡ ኀበ እግዚአብሔር ኵሎሙ አሕዛብ እለ ተሰምየ ስምየ ላዕሌሆሙ ይቤ እግዚአብሔር ፡፡

፻፯፤ወበእንተዝ እብለክሙ አነ ኢታ ክብዱ ዲበ አሕዛብ እለ ተመይጡ ኀበ እግዚአብሔር ፡፡

፻፪፤ከዚህም በኋላ ምእመናን ተነሥተው እግዚአብሔርን እስከ መቼ ድረስ ትፈታተኑታላችሁ አሕዛብንስ ሊሸከሙት የማይች ሉትን ከባድ ሸክም እስከ መቼ ታሸ ክሟቸዋላችሁ አሉ፡፡

፻፫፤ ነገር ግን እኛ በእግዚአ ብሔር ቸርነት እንደምንድን እናምናለን፣ "እንደዚሁ እግዚ አብሔር ከኃጢአት ማሰርያ ፈታን ከባድ ሸክምንም ከኛ ላይ አቀለለ፡፡

፻፬፤እንደዚህም ባለ ጊዜ ሕዝቡ ሁሉ ዝም አሉ፡፡

፻፭፤ከዚህም በኋላ የጌታችን ወን ድሙ ያዕቆብ እነሆ የምነግራ ችሁን ስሙ፣ ስምዖን እግዚ አብሔር ለሥርዓቱ ሕዝብን እንደመረጠ አስቀድሞ ተና ገረ ፡፡

፻፮፤ መጽሐፍ የፈረሰውን የዳዊትን ቤት መጥቼ እንፃለሁ እንዳለ በላያቸው ላዬ ስሜ የተጠራ አሕዛብ ሁሉ ወደ እግዚአብሔር ይመለሱ ዘንድ የወ ደቁትንም አነሣቸዋለሁ አለ እግዚአብሔር ፡፡

፻፯፤ ስለዚህም እኔ ወደ እግዚአ ብሔር በተመለሱ ሰዎች ላይ ሥርዓትን አታጽኑ እላችኋ ላሁ ፡፡

፺፰፤ ዳዕሙ አዝዝዎሙ ይርኀቁ እምኵሉ ርኵስ ወኢይብልዑ ማውታ ወዘይዘብሑ ለአማልክት ወእምዝሙት ዘኢእዙዝ ውስተ ሕግ ወዘሂ ጽሑፍ ውስተ መጽሐፈ አበው ሄኖስ ወሄኖክ ወኖኅ ወመልከ ጼዴቅ ወኢዮብ ወባዕዳንሂ እለ ከማሆሙ ::

፺፱፤ ወእምዝ ኀብሩ ሐዋርያት ወያዕቆብ ኤጲስ ቆጶስ ዘኢየሩሳሌም ወቀሲሳን ዘቤተ ክርስቲያን፣ ወኀረዩ እምኔነ ዕደወ ዘይፌንዉ ምስለ በርናባስ ወጳውሎስ ሰፋዩ ወይሁዳ ዘተሰምየ በርናባስ ወሲላስ እለ ተኀርዩ እምአኃው ::

፻፤ወእምዝ ጸሐፍነ ወፌነውነ ኀበ አኃው ውስተ ቤተ ክርስቲያን ዘአንጾኪያ ወሶርያ እንዘ ንብል ሰላም ለክሙ እስመ ሰማዕነ ከመ ቦ እለ ወጽኡ እምኔነ ወሆክዋ ለነፍስክሙ በነገር ዘኢአዘዝናሆሙ ::

፻፩፤ ወይእዜኒ ኀቢረነ ኀረይነ ዕደወ እለ ንፌኑ ኀቤክሙ ምስለ አኃዊነ በርናባስ ወጳውሎስ እለ መጠዉ ነፍሶሙ በእንተ ስመ ኢየሱስ ክርስቶስ ::

፺፰፤ከርኩስ ሁሉ ይርቁ ዘንድ ሙቶ ያደረውን ፣ ለአማልክትም የተሠዋውን እንዳይበሉ፣ በአባቶች በሄኖስ ፣ በሄኖክ ፣ በኖኅ ፣ በመልከ ጼድቅ ፣ በኢዮብ እንደነሱ ባሉ በሌሎችም መጽሐፍ ውስጥ ካልተጻፈ በሕግ ውስጥም ካልታዘዘ ከዝሙት ይርቁ ዘንድ እዘዟቸው እንጂ ::

፺፱፤ ከዚህም የኢሩሳሌም ኤጲስ ቆጶስ ያዕቆብና ሐዋርያት ፣ የቤተ ክርስቲያን ቀሳውስትም ከሰፊው ጳውሎስና ከበርናባስ ፣ ከወንድሞች ከተመረጡ ከሲላስና በርናባስ ከተባለ ይሁዳ ጋራ የሚልኳቸውን ሰዎች ከእኛ መረጡ ::

፻፤ከዚህም በኋላ ወደ አንጾኪያና ሶርያ ቤተ ክርስቲያን ወንድሞች ‹‹ሰላም ለእናንተ ይሁን›› ብለን ጽፈን ላክን ፣ ከእኛ ወጥተው ባላዘዝናቸው ነገር ሰውነታችሁን የሚያውኳት እንዳሉ ሰምተናልና::

፻፩፤ ዛሬም ከወንድሞቻችን ከጳውሎስና ከበርናባስ ጋራ ወደ ናንተ የምንልካቸው ስለ ኢየሱስ ክርስቶስ ስምም ሰውነታቸውን አሳልፈው ለሞት የሰጡ ሰዎችን አንድ ሁነን መረጥን::



፻፪፤ ወፌነውነ ይሁዳሃ ወሲላስሃ ያጠይቁክሙ እስመ ኀብረ መንፈስ ቅዱስ ምስሌነ ከመ ኢንወስክ ባዕደ ወኢናክብድ::

፻፫፤ ዘእንበለ ዳዕሙ ዘተኀድገ በግብር ዝቡሐ ለአማልክት ወማውታ ወደመ ወዝሙተ ወዘትጸልኡ ለርእስክሙ ኢትግበሩ ዲበ ቢጽክሙ ::

፻፬፤ ዘንተ ዕቀቡ ወሰላም ለክሙ ዛተ መልእክተ ለአክነ አንጾኪያ እስመ ብዙኀ መዋዕለ ሠራሕነ እንዘ ንፌቅድ ገቢረ ዘይሤኒ ለነ ወለክሙ [፫] ::

፻፭፤ ወእምድኅረ ኅዳጥ መዋዕል ሐወፅናሆሙ ለአኃው ወአጽናዕናሆሙ በቃለ ተግሣፅ ወአዘዝናሆሙ ይርኃቁ እምእለ ይጸርፉ ላዕለ ስመ እግዚአብሔር ወዲበ ሙሴ::

፻፮፤ እስመ እሙንቱ መሰጥ ወይትሜሰሉ ከመ አባግዐ ወይትቃረኑ ምስለ እግዚአብሔር ወሙሴ ወነቢያት ::

፻፯፤ሐሳውያነ መሲሕ ወሐሳውያነ ነቢያት ወሐዋርያት ወመስሕታን እለ የሀጕልዎሙ ለአሕዛብ ወያደንኑ ውስተ ምድር ወይሔልዩ ኵሎ እከየ ወያማስኑ ዐፀደ ወይን ቅዱሰ ::

[፫]፡ ግብ. ሐዋ. ፲፭ . ፳ - ፳፺

፻፪፤ይሁዳንና ሲላስንም ያስረዷችሁ ዘንድ ላክነ መንፈስ ቅዱስ ሌላ ሥርዓት እንዳንጨምርና እንዳናከብድ ከኛ ጋራ አንድ ሁኗልና::

፻፫፤በግብር ከምትተዋቸው ለአማልክት ከተሰጡ ፣ ሙቶ ካደረው ፣ ከደም ፣ ከመሰሰን በቀር፣ ለራሳችሁ የምትጠሉትንም በባልንጀራችሁ እንዳታደርጉ ነው እንጂ::

፻፬፤ይህን ጠብቁ ሰላምም ለናንተ ይሁን ፣ ይህችን መልእክት ወደ አንጾኪያ ላክነ ለናንተና ለኛ በጐ የሚሆን መሥራትን ስንሻ ብዙ ቀን ደክመናልና ::

፻፭፤ ከጥቂት ቀን በኋላም ወንድሞችን ጐብኝተን በምክር ቃል አጸናናቸው ፣ በሙሴና በእግዚአብሔር ስም ላይ ከሚሳደቡ ይርቁ ዘንድም አዘዝነ::

፻፮፤ እሊህ ነጣቂዎች ናቸውና እንደበጎችም እየተመሰሉ ከእግዚአብሔር ከሙሴና ከነቢያትም ጋር ያጣላሉና::

፻፯፤መሢሕ ክርስቶስን ነቢያትንና ሐዋርያትን የሚዋሹ ናቸው ፣ አሕዛብንም የሚያጠፉ አሳቾች ናቸው፣ ወደ ምድር አቀርቅረው ክፉን ሁሉ ያስባሉ፣ ቅዱሱንም የወይን ቦታን ያጠፋሉ ::

፳፰ ወበእንተ ዝንቱ እሉ የዐልዉ ፍቅሮሙ ለብዙኃን ወዘሰ አዝለፈ ትእግሥቶ ውእቱ ይድኅን ።

፳፱ ወበእንተ ዝንቱ አዘዘነ እግዚእነ እንዘ ይብል ተዓቀቡ እምሐሳውያነ ነቢያት እለ ይመጽኡ ኀቤክሙ በአልባሰ አባግዕ ወውስጦሙ ተኵላ ወመሰጥ እሙንቱ ወእምፍሬሆሙ ተአምርዎሙ ።

፴ ወእንበይነዝ ተጋባእነ ኵልነ ውስተ ፩ መካን ንሕነ እሙንቱ ሐዋርያቲሁ ለኢየሱስ ክርስቶስ።

፴፩ ጴጥሮስ ወእንድርያስ ፤ ያዕቆብ ወዮሐንስ ደቂቀ ዘብዴዎስ፤ ፊልጶስ ፤ ወበርተሎሜዎስ፤ማቴዎስ ወቶማስ ፤ ያዕቆብ ወልደ እልፍዮስ ወስምዖን ቀነናዊ ፤ ታዴዎስ ወማትያስ ዘተኈለቈ ምስሌነ ወተሠይመ ህየንተ ይሁዳ አስቆሮታዊ ፤ ወያዕቆብ እኁሁ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ኤጲስ ቆጶስ ዘኢየሩሳሌም ፤ ወጳውሎስ ኄር ወመገሥጽ ለአሕዛብ ።

፴፪ ወእንዘ ጉቡኣን ንሕነ ውስተ ፩ መካን ፈነውነ ኀቤክሙ ዛተ መልእክተ ቅድስተ።

፴፫ ወአንትሙኒ ኦ መሃይምናን አኃው እለ አመንክሙ በክርስቶስ ዘቦቱ ኵሉ ኮነ ወይእዜኒ ንብለክሙ ከመ ውእቱ ፩ አምላክ አኃዜ ኵሉ ወአልቦ ባዕድ አምላክ ዘእንበሌሁ።

፳፰ ስለዚህም እነዚህ የብዙዎችን ፍቅር ይለውጣሉ ፤ ትዕግሥትን ያዘወተረ ግን እርሱ ይድናል ።

፳፱ ስለዚህም ነገር ጌታችን ነቢያትን ሐሰተኞች ከሚያደርጉ ውስጣቸውም የሚነጣጥቁ ተኵላዎች ሲሆኑ የበግ ለምድ ለብሰው ወደ እናንተ ከሚመጡ ተጠበቁ ብሎ አዘዘን ፤ ከሥራቸውም የተነሣ ታውቋቸዋላችሁ ።

፴ ስለዚህም እኛ የኢየሱስ ክርስቶስ መልእክተኞች የሆንነ እኛ ሁላችን በአንድ ቦታ ተሰበሰብን።

፴፩ እንድርያስና ጴጥሮስ፤የዘብዴዎስም ልጆች ዮሐንስና ያዕቆብ፤ በርተሎሜዎስና ፊልጶስ ፤ ቶማስና ማቴዎስ ፤ የቃና ሰው ስምዖንና የዕልፍዮስ ልጅ ያዕቆብ ፤ ስለ አስቆሮት ሰው ይሁዳ ፈንታ ተሹሞ ከኛ ጋራ የተቈጠረ ማትያስና ታዴዎስ ፤ የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ወንድሙ የኢየሩሳሌም ኤጲስ ቆጶስ ያዕቆብ፤ ለአሕዛብ የሚመክር ቸር ጳውሎስ ።

፴፪ እኛም ከአንድ ቦታ ተሰብስበን ሳለ ክብርት የምትሆን ይህችን መልእክት ወደ ናንተ ላክን።

፴፫ እናንተም ሁሉ በእርሱ ቃል ነት በተፈጠረ በክርስቶስ ያመናችሁ ወንድሞች ምእመናን ሆይ፤ አሁንም ሁሉን የፈጠረ አንድ አምላክ እንደ ሆነ ያለ እርሱም ሌላ አምላክ እንደሌለ እንነግራችኋለን።



፴፬ ንሜህረክሙ ታምልኩ ኪያሁ ወትስግዱ ሎቱ ወትትቀነዩ ለኢየሱስ ክርስቶስ ወመንፈስ ቅዱስ ወታንብቡ ቅዱሳተ ፤ መጻሕፍተ ኦሪት ወነቢያት።

፴፭ ወአክብሩ አበዊክሙ ወተገኃሡ እምኵሉ ዘይትቃረን ተቃርኖ ምስለ ሕግ ወአንትሙሰ እመኑ ትንሣኤ ወዕለተ ኵነኔ።

፴፮ ወጽንሑ ከመ ይፈድዮ ለኵሉ በከመ ምግባሩ ፤ እስመ ኵሉ ፍጥረት እምእግዚአብሔር ውእቱ ወኢኮነ እምሰይጣን።

፴፯ ወባሕቱ ኵሉ እኩይ እምሰይጣን ውእቱ ።

፴፰ ወሰብሳብሰ ዘበሕግ አልቦ ነውር ወኢሕፀት አላ ዳዕሙ እምእግዚአብሔር ውእቱ እስመ ፈጠረ ቀዲሙ ተባዕተ ወአንስተ[፪]።

፴፱ ወበእንተዝ ይቤ የኀድግ ብእሲ አባሁ ወእሞ ወይተልዋ ለብእሲቱ ወይከውኑ ፪ኤሆሙ ፩ ሥጋ[፫] ።

፵ ወእምድኅረሰ አውሰበ ኢይድኅር ብእሲ ብእሲቶ ዘእንበለ በዝሙት ባሕቲቱ ፤ እስመ ሥጋሁ ይእቲ እስመ አነ ፈጠርክዎሙ ወአኮ ባዕድ ።

፴፬ እሱን ታመልኩ ዘንድ ለእርሱም ትሰግዱ ዘንድ ፤ ለኢየሱስ ክርስቶስና ለመንፈስ ቅዱስም ትገዙ ፤ ዘንድ ቅዱሳት መጻሕፍትን ኦሪትንና ነቢያትንም ታነብቡ ዘንድ እናስተምራችኋለን።

፴፭ አባቶቻችሁን አክብሩ ከሕግ ጋራ መቃወምን ከሚቃወም ሁሉ ተለዩ ፤ እናንተስ ትንሣኤንና የፍርድ ቀንን እመኑ ።

፴፮ ለሁሉ እንደሥራው እንደሚከፍለው ጠብቁ ፤ ፍጥረት ሁሉ ከእግዚአብሔር ተገኝቷልና ከሰይጣንም አይደለም ።

፴፯ ነገር ግን ክፉ ሁሉ ከሰይጣን ነው።

፴፰ በሕግ የሚሆን ጋብቻም ነውርና ጉድለት የለበትም ፤ ከእግዚአብሔር የታዘዘ ነው እንጂ አስቀድሞ ወንድና ሴት አድርጎ ፈጥሮአቸዋልና ።

፴፱ ስለዚህም እንዲህ አለ ፤ ሰው እናትና አባቱን ትቶ ሚስቱን ይከተላታል ፤ ሁለቱም አንድ አካልን ይሆናሉ ።

፵ ካገባም በኋላ በዝሙት ብቻ እንጂ ሰው ሚስቱን አይፍታ ፤ አካሉ ናትና ፤ እኔ ፈጥሬያቸዋለሁና ሌላም አይደለም ።

፪ ዘፍ. ፩ : ፳፯

፹፩፡ይቤ ዘእግዚአብሔር አስተዓመረ ኢይፍልጥ ሰብእ እስመ ዘይትፌለጥ እምብእሲቱ እንዘ ይሬሲ ፪ ሥጋ ዐለወ ትእዛዘ እግዚአብሔር[፩]፡፡

፹፪፡ወዘሂ አውሰበ ድኅርተ አርኰሰ ሥጋሁ ወዘተለዋ ለዘማ ዐለወ ሕገ ግሙራ፡፡

፹፫፡ ምትራ ለዘማ እምሥጋከ እስመ ኢኮነት እንቲአከ፡፡

፹፬፡ ኢታርኵሱ እንከ ሥጋክሙ እስመ የአክሎሙ ለመሃይምናን ግዝረተ ልብ በንጹሕ መንፈስ ፡፡

፹፭፡ኢትረስዩ ፪ተ ጥምቀተ የአክለክሙ ዘነሣእክሙ ቀዳሚ ጥምቀት ፡፡

፹፮፡ እስመ ተቀበርክሙ ውስተ ሞቱ ለክርስቶስ እንተ ኢተውህበት ለዕልዋን ወመናፍቃን አላ ዳዕሙ ለቅዱሳን ካህናት ዘጸገውናክሙ በስመ አብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ፡፡

፹፯፡ ወኢትትወከፉ ጥምቀተ እምነበ ዕልዋነ ሃይማኖት ፡ እስመ አሐቲ ይእቲ ጥምቀት ወአሐዱ እግዚአብሔር አብ ፡ ወእግዚእነ ወመድኀኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወጰራቅሊጦስ መንፈስ ቅዱስ ፩[፮] ውእቱ ሞቱ ለኢየሱስ ክርስቶስ በሥጋ ፡፡

፩ ማቴ. ፲፱ ፡ ፯ - ፱
፮ ኤፌ. ፬ ፡ ፬ - ፯

፹፩፡ እንዲህም አለ ፣ እግዚአብሔር አንድ ያደረገውን ሰው አይለይ ፤ ሁለት አካል አድርጎ ከሚስቱ የሚለይ ሰው የእግዚአብሔርን ትእዛዝ አፈረሰ ፡፡

፹፪፡የተፋታቸውንም ያገባ ሥጋውን አረከሰ ፤ ዘማዊቲቱንም የተከተለ ፈጽሞ ሕግን አፈረሰ፡፡

፹፫፡ዘማዊቲቱን ከሥጋህ ለያት፤ ያንተ አልሆነችምና ፡፡

፹፬፡እንግዲህ ሥጋችሁን አታርክሱ ፤ ለምእመናን በንጹሕ መንፈስ የልብ መገረዝ ይበቃቸዋልና፡፡

፹፭፡ሁለተኛ ጥምቀትን አታድርጉ ፤ መጀመርያ የተጠመቃችሁት ይበቃችኋል ፡፡

፹፮፡በክርስቶስ ሞት ተቀብራችኋልና (ተጠምቃችኋልና) ለከሐዲዎችና ለመናፍቃን ያልተሰጠች፣ ነገር ግን ለቅዱሳን ካህናት በአብ በወልድ በመንፈስ ቅዱስ ስም የሰጠናችሁ ናት ፡፡

፹፯፡ሃይማኖትን ከለወጡ ሰዎች ጥምቀትን አትቀበሉ፣ጥምቀት አንዲት ናትና እግዚአብሔር አብ አንድ ነው፣ ጌታችንና መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስም አንድ ነው ፣ መንፈስ ቅዱስ ጰራቅሊጦስም አንድ ነው ፣ ኢየሱስ ክርስቶስም በሥጋ የሞተው ሞት አንድ ነው፡፡



፹፰፡ ወከማሁ ይኩን ጥምቀትክሙ ፩ዱ ዘነሣእክሙ በሞቱ፡፡

፹፱፡ወዘሰ ኢየአምን ወኢይገብር ከመዝ ይከውን ክፍሉ ምስለ ዕልዋን ውስተ ትምህርት እኩይ፡፡

፺፡ወለእለ ይገብሩ ከመዝ ይቤ እግዚአብሔር እስመ መነንክሙ ትምህርትየ ወአነሂ እሜንነክሙ ወአንገድክሙ ወኢይሬስየክሙ ሊቃነ ካህናት ፡፡

፺፩፡ ወእለ ይጠመቁሂ እምኔክሙ ኢኮኑ ንጹሐነ አላ ዳዕሙ ርኩሳን ወአልቦሙ ሥርየተ ኃጢአት፡፡

፺፪፡ከማሁ ይከውኑ እለ ይነሥኡ ፪ ጥምቀተ ወይሬስዩ ግብሮ ለክርስቶስ ተውኔተ ወይትሜየንዎሙ ለቅዱሳን ወይፀርፉ ላዕለ መንፈስ ቅዱስ ወያረኵሱ ደሞ ክቡረ ወየዐልዉ ሕማማቲሁ ወስምዖ፡፡

፺፫፡ ወእለሰ ኢየአምኑ ወኢይጠመቁ በርትዕት ሃይማኖት ይከውኑ ውጉዛነ እምሕግ ወይትኴነኑ እስመ እሙንቱ ይጸዕልዎ ወኢየአኩትዎ፡፡

፹፰፡ እንዲሁ በሞቱ አምሳል የተቀበላችሁት ጥምቀትም አንድ ጊዜ ይሁን ፡፡

፹፱፡ ነገር ግን የማያምን እንደዚህም የሚያደርግ ክፍሉ ከከሐዲዎችና ክፉ ትምህርት ከአላቸው ጋር ይሆናል፡፡

፺፡እንደዚህ ለሚያደርጉ ሰዎችም እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፣ «ትምህርቴን ንቃችኋልና ፣ እኔም እንቃችኋለሁ ፣ እተዋችኋለሁ የካህናት አለቆችም አላደርጋችሁም፡፡»

፺፩፡ ከናንተም የሚጠመቁት ንጹሓን አይደሉም፣የኃጢአት ሥርየት የሌላቸው ርኩሳን ናቸው እንጂ፡፡

፺፪፡ ሁለተኛ ጥምቀትን የሚቀበሉም እንዲሁ ይሆናሉ፣ የክርስቶስንም ሥራ ጨዋታ ያደርጋሉ፣ ቅዱሳንንም ይተናኰሏቸዋል፣ በመንፈስ ቅዱስ ላይም ይሳደባሉ፣ ክቡር ደሙንም ያረክሳሉ፣ መከራዎቹንና ምስክርነቱንም ይክዳሉ ፡፡

፺፫፡ በቀናች ሃይማኖት አምነው የማይጠመቁ ግን ከሕግ የወጡ ይሆናሉ ይፈረድባቸዋልም፣እነርሱ ይሰድቡታል እንጂ አያምኑበትምና፡፡

፺፬፡ ይቤ እግዚእነ ዘኢ ተወልደ ዳግመ እማይ ወእመንፈስ ቅዱስ ኢይክል በዊአ መንግሥተ ሰማያት አላ ዳዕሙ ዘአምነ ወዘተጠምቀ ይድኅን ወዘሰ ኢየአምን ይትኴነን [1]::

፺፭፡ ወዘሰ ይብል ድኅረ እጠመቅ ወያጸርዕ ጥምቀተ ውእቱ ይትኴነን ወይርኅቅ እምእግዚአብሔር::

፺፮፡ ወኢትትሀከዩ ተመይጦ ኀበ እግዚአብሔር እስመ ኢየአምር ሰብእ ዘይመጽእ ላዕሌሁ ::

፺፯፡ ወአንትሙሰ አጥምቁ ደቂቀክሙ እንዘ ሕፃናት እሙንቱ ወሴስይዎሙ ሲሳየ መንፈሳዊተ ወሕፅንዎሙ በተግሣጽ ወጥበብ::

፺፰፡ እስመ ይቤ ኀድግዎሙ ለሕፃናት ወኢትክልዕዎሙ መጺአ ኀቤየ [2] ::

፺፱፡ናሁ ጸሐፍነ ለክሙ ዘንተ ኵሎ አ ፍቁራን አኃው ትለብዉ ጥበበ ወአእምሮ ወኢትትወከፉ ነገረ ፅሩዐ ዘገብሩ ዕልዋን በስመ ዚአነ::

፻፡ኢትበሉ እንከ ብነ ሐዋርያት እለ ይስእሉ በእንቲአነ አላ ዳዕሙ ነጽሩ ሥነ ግብሮሙ::

፺፬፡ጌታችን ዳግመኛ ከውሀና ከመንፈስ ቅዱስ ያልተወለደ ወደ መንግሥተ ሰማያት መግባት አይችልም ፣ ነገር ግን ያመነና የተጠመቀ ይድናል ያላመነ ግን ይፈረድበታል አለ::

፺፭፡ኋላ እጠመቃለሁ ብሎ ጥምቀትን የሚያስቀር ግን ይፈረድበታል፣ከእግዚአብሔርም ይርቃል::

፺፮፡ወደ እግዚአብሔር መመለስን ችላ አትበሉ ሰው በላዩ የሚመጣበትን አያውቅምና ::

፺፯፡እናንተ ግን ልጆቻችሁን ሕፃናት ሳሉ አጥምቁ ፣ መንፈሳዊ ምግብንም መግቧቸው ፣ በምክርና በጥበብም አሳድጓቸው::

፺፰፡ ልጆችን ተዋቸው ፣ ወደኔ መምጣትንም አትከልክሏቸው ብሏልና::

፺፱፡ የተወደዳችሁ ወንድሞች ሆይ ፣ ጥበብንና ዕውቀትን ታስተውሉ ዘንድ ይህን ሁሉ ጻፍንላችሁ ወንጀለኞች በእኛ ስም የሚያደርጉትን ተርታ ነገርንም አትቀበሉ ::

፻፡እንግዲህም ስለ እኛ የሚለምኑ ሐዋርያት አሉን አትበሉ ፣ የሥራቸውን ደግነት ተመልከቱ እንጂ ::

[1] ዮሐ. ፫ ፡ ፭ - ፱
[2] ማቴ ፲፱ - ፲፬



፻፩፡እስመ ቦ እለ ይገብሩ ብዙኀ ኀይላተ ዘምሉዕ ኀምዘ ሞት በስሙ ለኢየሱስ ክርቶስ ከመ ሲሞን መሠርይ ወከላዮፊዮስ ወእለ ምስሌሆሙ በኵሉ መካን እለ ያስሕትዎሙ ለሰብእ [3]::

፻፪፡ወአንትሙኒ እለ አፍቀርክምዎ ለክርስቶስ ወንሕነ አግብርቲሁ ወላእካኒሁ እሙንቱ ቀደምት ጸሐፍነ መጻሕፍተ ዕፁባተ ዘሙሴ ወሄኖክ፣ ወአዳም ወሴት፣ ወኢሳይያስ ወዳዊት ፣ ወኤልያስ ወ፫ቱ አበው ቀደምት፣ወእለ ይትቃረንዎሙ ለእሉ ይከውኑ ውፁዓነ እምሕግ ::

፻፫፡ወዓዲ ጸሐፉ መጽሐፈ በስመ ጽርዕ እለ ይሬስዩ ርእሶሙ ኅሩያነ ወንጹሓነ ወይብሉ ጥዩቅ ውእቱ መጻሕፍቲነ እንዘ ርኵሳን እሙንቱ ረኀቁ እምኔሆሙ ወእም እለ ይገብሩ ከመዝ::

፻፬፡ከመ ኢትትኰነኑ ምስሌሆሙ እለ ጸሐፉ ለአስሕቶ መሃይምናን ዘአልቦሙ ነውር ::

፻፭፡ አርዳኢሁ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ንቤ እንከ በእንተ ኤጲስ ቆጶሳት ወቀሳውስት ወዲያቆናት ይንበሩ በአሐቲ ብእሲት እምቅድመ ሢመት፣ ወእምድኅረ ሢመትሰ ኢርቱዕ ያውስቡ ::

፻፩፡የሞት መርዝን የተመላ ብዙ ታምራትን በኢየሱስ ክርስቶስ ስም የሚአደርጉ አሉና ፣ እንደ ባለሥራዩ ሲሞንና እንደ ከላዮፊዮስ በቦታውም ሁሉ ከእነርሱ ጋር ሰዎችን የሚያስቷቸው አሉና ::

፻፪፡ ክርስቶስን የወደዳችሁት እናንተ እኛም ባርያዎቹ የቀደሙ እነዚያ አገልጋዮችም የሙሴንና የሄኖክን ፣ የአዳምንና የሴትን ፣ የኢሳይያስንና የዳዊትን ፣ የኤልያስንና የቀደሙ የሦስቱን አበው ድንቅ ድንቅ መጻሕፍትን ጻፍን፣ እሊህን የሚቃወሙ ከሕግ የወጡ ይሆናሉ ::

፻፫፡ዳግመኛም ራሳቸውን የተመረጡና ንጹሓን የሚያደርጉ በጽርዕ ስም መጽሐፍን ጻፉ፣ እነርሱ ርኵሳን ሲሆኑ መጽሐፎቻችንን የተረዱ ናቸው ይላሉ፣ ከእነርሱና እንዲህ ከሚያደርጉ ራቁ ::

፻፬፡ ነውር የሌላቸው ምእመናንን ለማሳት መጽሐፍን ከጻፉ ጋራ እንዳይፈረድባችሁ::

፻፭፡ የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ደቀ መዛሙርት እኛ ፣ ስለ ኤጲስ ቆጶሳትና ስለ ቀሳውስት ስለ ዲያቆናትም ከሹመት አስቀድመው በአንዲት ሴት ጸንተው ይኑሩ ፣ ከሹመት በኋላ ግን ሊያገቡ አይገባም አልን::

[3] የሐ ሥራ ፱ ፡ ፲፰ - ፳፬

፻፮፤ወካዕበ ንኤዝዝ በእንተ አግብርት እለ ይትኤዘዙ ለቤተክርስቲያን ንፍቀ ዲያቆናት አናጕንስጢስ ወዐጸውተ ኆዋኅው ይንበሩ በአሐቲ ብእሲት ወሰብሳብ ንጹሕ።

፻፯፤ወእምድኅረ ነሥኡስ ጥምቀተ ወሢመተ ኢይግበሩ ኃጢአተ ከመ ኢይረዱ ውስተ ኵነኔ ።

፻፰፤ናሁ ንኤዝዝ ከመ ኢያውስቡ ዘማ ወኢአመተ ወኢድኅርተ ወኢ መዐስብተ በከመ ጽሑፍ ውስተ ሕግ[፱]።

፻፱፤ ወዓዲ ዲያቆናዊት ብእሲት ትኩን ድንግለ ወንጽሕተ ፣ ወእመሂ መበለት መሃይምንት እንተ አውሰበት ፩ደ ብእሴ መፍትው ትርከብ ሢመተ አንስት።

፻፲፤ ወለእለሂ ይትመየጡ እም ኀጢአት ርቱዕ ትትወከፍዎሙ ዝውእቱ ፈቃዱ ለእግዚአብሔር በኢየሱስ ክርስቶስ ወለንዑሰ ክርስቲያንሂ።

፻፲፩፤ ሶበ ለበዉ ተግሣጸ አጥምቅዎሙ በስመ አብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ ።

፱ ፥ ፩ ጢሞ. ፫፥ ፩-፲፩ ፤ ቲቶ. ፩፥፫-፱፤ማቴ. ፲፱-፱

፻፮፤ሁለተኛም በቤተ ክርስቲያን ስለሚታዘዙ አገልጋዮች ንፍቀ ዲያቆናትና አናጕንስጢስ ስለ አፀውተ አናቅጽም በንጹሕ ጋብቻ በአንዲት ሴት ጸንተው ይኖሩ ዘንድ እናዝዛለን።

፻፯፤ጥምቀትንና ሹመትን ከተቀበሉ በኋላ ግን ወደ ቅጣት ፍርድ እንዳይወርዱ ኃጢአትን አይሥሩ ።

፻፰፤ እነሆ በሕግ እንደተጻፈ ዘማይቱን ፣ ነፃ ያልወጣች ባርያን፣ በነውር የተፈታችውን፣ ባሏ ሙቶባት የገለሞተችውን እንዳያገቡ እናዝዛለን።

፻፱፤ዳግመኛም ዲያቆናዊት ሴት ንጽሕት ድንግል ትሁን ፣ ፈትም ብትሆን አንድ ሰውን ያገባች የታመነች የሴቶችን ሹመት ታገኝ ዘንድ ይገባል።

፻፲፤ ከኃጢአት የሚመለሱትንም ትቀበሉአቸው ዘንድ አግባብ ነው፣ በኢየሱስ ክርስቶስ የእግዚአብሔር ፈቃዱ ይህ ነውና ፣ ንዑሰ ክርስቲያንንም ተቀበሉአቸው ።

፻፲፩፤ ትምህርትንም በተረዱ ጊዜ በአብ በወልድ በመንፈስ ቅዱስ ስም አጥምቋቸው ።



፻፲፪፤ ወለእለሰ አልቦሙ አምልኮ እግዚአብሔር አዝዝዎሙ ለመሃይምናን ይትፈለጡ እምኔሆሙ በኵሉ ግብር ኢበምክር ወኢበነገር ወኢበጸልዮ ወአርኅቅዎሙ እምቤተ ክርስቲያን ዘእግዚአብሔር እስመ ነኪራን እሙንቱ ወእኩያን ወሙሱናን እለ የሀጕሉ አባግዐ መርዔቱ ለክርስቶስ ።

፻፲፫፤ወበእንቲአሆሙ ይቤ ጠቢብ ሰሎሞን አሌ ሎሙ ለመናፍቃን እለ ያጠብቡ ርእሶሙ ወደኃሪቶሙ ለኵነኔ ሲኦል እሉ እሙንቱ እለ ይሜህሩ ተግሣፀ ሐሰት ወይፀርፉ ዲበ መንፈስ ቅዱስ ወእለ ተሀይደ እምኔሆሙ ክፍለ ርስት ዘነሥኡ እምኀቤሁ ወአልቦሙ ስርየት በዝ ዓለም ወኢበዘይመጽእ ዓለም ።

፻፲፬፤ እስመ አፈድፈዱ ዐሊወ እምአይሁድ ወአረማውያን እለ ይፀርፉ ላዕለ እግዚአብሔር ፈጣሬ ኵሉ ወውእቱ መልዕልተ ኵሉ ወተንሥኡ ላዕለ ወልዱ ወክሕድዎ ለመንፈስ ቅዱስ ወአፅርዑ መጻሕፍተ ቅዱሳተ ወኀረዩ ሎሙ ፅርፈተ ወአማሰኑ ቤተ ክርስቲያኑ ለክርስቶስ እሉ እሙንቱ ቈናጽል እለ ያማስኑ ዐጸደ ወይን።

፻፲፪፤እግዚአብሔርን ማምለክ የሌለባቸውን ግን ምዕመናን በሥራው ሁሉ በምክር ቢሆን ፣ በነገርም ቢሆን ፣ በጸሎትም ቢሆን ፣ ከእነርሱ ይለዩ ዘንድ እዘዟቸው፣ከእግዚአብሔርም ቤተ ክርስቲያን አርቋቸው ፣ እነርሱ የተለዩ ክፉዎች የጠፉ የክርስቶስን መንጋዎች የሚአጠፉ ናቸውና ።

፻፲፫፤ ስለ እነርሱም ጠቢቡ ሰሎሞን እንዲህ አለ ፤ ራሳቸውን ጥበበኛ ለሚያደርጉ ሰዎች ወዮላቸው፣ ፍጻሜአቸውም ለሲኦል ቅጣት ነው ፣ እሊኽውም የሐሰት ምክርን የሚአስተምሩ በመንፈስ ቅዱስ ላይም የሚሳደቡ ፣ ከእርሱ የተቀበሉት የርስት ክፍልም ከእነርሱ የተቀማ በዚህ ዓለም በሚመጣውም ዓለም የኃጢአት ሥርየት የሌላቸው ናቸው ።

፻፲፬፤ሁሉን በፈጠረ ከሁሉ በላይ በሚሆን በእግዚአብሔር አብ ላይ ከሚሳደቡ በልጁም ላይ ከተነሡ መንፈስ ቅዱስንም ከካዱ ፣ ስድብንም ለነሱ መርጠው ቅዱሳት መጻሕፍትን ካስታጐሉ ፣ እሊኸውም የወይን ቦታን የሚያጠፉ ቀበሮዎች ናቸው ፣ የክርስቶስ ማደሪያ ቤተ ክርስቲያንን ከሚያጠፉ ከወንጀለኞች ከአይሁድ ይልቅ ክህደትን አብዝተዋልና።

፻፲፭፡ ንኤዝዘክሙ ረኀቁ እምእሉ እስመ ዘይተሉ ጠቢበ ይከውን ከመ ውእቱ ጠቢብ ወዘሂ ይተሉ አብደ ይከውን ከመ ውእቱ አብድ።

፻፲፮፡ ኢመፍትው ከመ ትንበሩ ምስለ ሰረቅት ወኢትደመሩ ምስለ ዐላውያን።

፻፲፯፡ ስምዑ ዘይቤ ዳዊት ቅዱስ አኮኑ ጸላእተከ ጸላእኩ እግዚኦ ወተመንሰውኩ በእንተ ፀርከ ፍጹመ ጽልአ ጸላእክዎሙ ወኮኑኒ ፀርየ[፲]።

፻፲፰፡ እስመ ረገሞ እግዚአብሔር ለኢዮሳፍጥ በእንተ ፍቅር ወረድኤተ አክዓብ ንጉሥ ወአካዝያስ።

፻፲፱ ይቤሎ ለንጉሥ ኢዩ ነቢይ ኮንከ ረድኦ ለብእሲ ኃጥእ ታድኅኖኑ እንከ አንተ ዘጸልአ እግዚአብሔር[፲፩]።

፻፳፡ ወበእንተዝ ወረደ ፍጡነ መዓተ እግዚአብሔር ላዕሌሁ እስመ ኢኮነ ርቱዐ ልቡ በቅድሜሁ ወኮነ ኅሡረ ምግባሩ በውስተ ምድር[፲፪]።

፻፳፩፡ ረኀቁ እንከ እምኔሆሙ ወኢትትወከፉ ሰላሞሙ።

፻፳፪፡ ወበእንቲአሆሙ ይቤ ነቢይ አልቦሙ ፍሥሓ ለረሲዓን በቅድመ እግዚአብሔር እሉ እሙንቱ ተኵላት ወከለባት መሰጥ እለ አልቦሙ ምሕረት[፲፫]።

፲ መዝ. ፻፴፰ - ፳፩ - ፳፪
፲፩ + ፪ ዜና መዋ. ፲፱ - ፪
፲፪— ፪ ዜና መዋ. ፳ - ፴፯
፲፫ ፡ ኢሳ. ፶፯ - ፳፩

፻፲፭፡ ከእሊህ ትርቁ ዘንድ እናዝዛችኋለን ጥበበኛን የሚከተል እንደዚያ ጥበበኛን ይሆናልና አላዋቂንም የሚከተል እንደዚያ አላዋቂ ይሆናልና።

፻፲፮፡ ከሌቦች ጋራ ትኖሩ ዘንድ አገባብ አይደለም ፤ ከዓላውያን ጋራም አንድ አትሁኑ።

፻፲፯፡ ቅዱስ ዳዊት የሚለውን ስሙ አቤቱ ጠላቶችህን የጠላሁ አይደለሁምን ፤ ስለጠላቶችህም ጠፋሁ ፤ ፍጹም ጥልንም ጠላኋቸው ጠላትም ሆኑኝ።

፻፲፰፡ እግዚአብሔር ኢዮሳፍጥን፣ ንጉሥ አክዓብንና አካዝያስን ስለ ወደደና ስለ ረዳ ረግሞታልና።

፻፲፱፡ ንጉሡን ነቢዩ ፤ ኢዩም እንዲህ አለው ፤ የኃጢአተኛ ሰው ረዳትን ሆንህ ፤ እንግዲህ እግዚአብሔር የጠላውን አንተ ታድነዋለህን።

፻፳፡ ስለዚህም የእግዚአብሔር ቁጣ ፈጥኖ በእርሱ ላይ ወረደ ፤ ልቡ በፊቱ የቀና አልሆነምና ፤ በምድርም ሥራው ወራዳ ሁኗልና ።

፻፳፩፡ እንኪያስ ከእነርሱ ራቁ ሰላማቸውንም አትመኑ።

፻፳፪፡ ስለ እነርሱም ነቢይ እንዲህ አለ ፤ ለዝንጉዎች ሰዎች በእግዚአብሔር ፊት ደስታ የላቸውም ፤ እነርሱም ምሕረት የሌላቸው ተኵላዎችና ነጣቂዎች ውሾች ናቸው።



፻፳፫፡ ወሶበ ቀርበት ዕለት ወበጽሐት ሰዓት ብዙኃን ይከውኑ እኩያነ ።

፻፳፬፡ በከመ ይቤ እግዚእነ በወንጌል ወበደኃሪ መዋዕል ተሐፅፅ ሃይማኖት ወትሴኵስ ፍቅር ወትበዝኅ ኃጢአት ወይመጽኡ ሐሳውያነ መሲሕ ወሐሳውያነ ነቢያት ወይገብሩ ተአምረ በውስተ ሰማይ ወያስኍትዎሙ ለብዙኃን ኅሩያን።

፻፳፭፡ ናሁኬ ንስእሎ ለእግዚአብሔር ያድኅነነ እምስሕተቶሙ በኢየሱስ ክርስቶስ ወይባልሐነ እምዕልዋን ሕዝብ ከመ ናጽንዓ ለቤተ ክርስቲያን ወያድኅኖሙ ለብዙኃን ወይፈውሶሙ በብዙኅ ተግሣፅ ወበቃለ ጸጋ[፲፬] ።

፻፳፮፡ ወእለሰ ኢተወክፉ ስብከተነ ስዕኑ ተፈውሶ ወወፅኡ እመርዔት ከመ ያማስኑ ካልኣነ አባግዐ ንጹሓነ እለ አልቦሙ ነውር።

፻፳፯፡ ወከመዝ ሠራዕነ እንከ በውስተ ኵሉ በሐውርት ወረሰይነ ለክሙ ዛተ ርትዕተ ትምህርተ /ዲድስቅልያ/ በጽድቅ ወበንጽሕ ተዝካረ ለእለ የአምኑ በእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወፈነውነ ምስለ ኅሩይ ቀሌምንጦስ ወፍቁር በርናባስ ወፍቁር ወልድ ጢሞቴዎስ ወብፁዕ ማርቆስ ወምስሌሆሙ ቲቶ ወሉቃስ ወአሶን ወሉኪዮስ ወሱሲ ጴጥሮስ[፲፭]።

፲፬ ማቴ. ፳፬ - ፲፪ - ፳፬
፲፭ + ሮሜ. ፲፮ - ፳፩

፻፳፫፡ ቀን በቀረበች ጊዜ ሰዓትም በደረሰች ጊዜ ብዙዎች ክፉዎችን ይሆናሉ ።

፻፳፬፡ ጌታችን በወንጌል እንደ አለ፣ በኋለኛው ዘመን ሃይማኖት ታንሳለች ፤ ፍቅርም ትጠፋለች፣ ኃጢአትም ትበዛለች ፤ በመሢሕ ክርስቶስ የሚዋሹ ፤ በነቢያትም የሚዋሹ ይመጣሉ ፤ በሰማይም ተአምርን ያደርጋሉ ብዙዎች ምርጦችንም ያስታሉ ።

፻፳፭፡ እነሆ እንግዲህ በኢየሱስ ክርስቶስ ከስሕተታቸው ያድነን ዘንድ እግዚአብሔርን እንለምነው ቤተ ክርስቲያንንም እንድናጸናት ከከዳተኞች ሕዝብ ይታደገን ዘንድ ብዙዎችንም ያድናቸውና ቡብዙ ምክርና በጸጋ ቃል ይፈውሳቸው ዘንድ እንለምነው።

፻፳፮፡ ትምህርታችንን ያልተቀበሉ ግን መዳን ተሳናቸው ፤ ነውር የሌለባቸው ሌሎች ንጹሓን በጎችን ያጠፉ ዘንድም ከመንጋ ወጡ ።

፻፳፯፡ እንግዲህ በቦታቸው ሁሉ እንዲህ ሠራን ፤ ይህችን የቀናች ትምህርትንም /ዲድስቅልያ/ በጽድቅና በንጽሕና በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ለሚያምኑ ሰዎች መታሰቢያ አደረግንላችሁ ፤ ከተመረጠ ቀሌምንጦስና ከተወደደ በርናባስ፣ ከተወደደ ልጅ ጢሞቴዎስና ከብፁዕ ማርቆስ፣ ከእነርሱም ጋር ከቲቶና ከሉቃስ ፤ ከአሶንና ከሉኪዮስ ፤ ከሱሲ ጴጥሮስም ጋር ላክነው ።

፻፷፰፤ ንስእለክሙ ትትመሰሉ በእሉ ወስምዑ ቃሎሙ ወረኃቁ እምዘ ትካት ልማድ እስመ ቀደ ምትሰ ኃለፉ ::

፻፷፱፤ ወአንትሙ ኩኑ ሐዲሳነ እስመ አእመርክምዎ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ዘቦቱ ኵሉ ኮነ ወወሀበነ ሕገ ንጹሐ ወመድ ኀኒተ ነፍስነ ዘረስይነ ውስቴታ ፍጹመ ስመ ዚአሁ ዘእንበለ ፍል ጠት ወሕፀት ወወልጦት ዘአልቦ ነውር እንተ ትመይጥ ነፍሳተ::

፻፸፤ ዘንተ ለዘረስዑ ዕብራውያን ወሀቦሙ ተዝካረ በሚልክያስ ነቢይ ዘይብል ተዘከሩ ሕገ ሙሴ ብእሴ እግዚአብሔር ዘአዘዘክሙ ዘንተ ትእዛዘ ጽድቅ ወቅድሳተ[፲፮]::

፻፸፩፤ ወእግዚእነ ኢሠዐረ ሕገ ኦሪት ወኢያሕፀፀ አላ ዳዕሙ ይቤ ኢተኀልፍ አሐቲ ቃል እምኦሪት እስከ ዝ ኵሉ ይትገበር ፤ ወካዕበ ይቤ ኢመጻእኩ እሥዐሮሙ ለኦ ሪት ወለነቢያት አላ ከመ እፈ ጽሞሙ[፲፯]::

፻፸፪፤ እስመ ሙሴ ሠራዔ ሕግ ነቢይ ወንጉሥ ፤ ወኤልያስ ነቢይ ቀናዒ አስተርአዩ ምስለ እግዚእ ሶበ ተወለጠ ራእዩ በቅድሜሆሙ ስምሀ ኮኑ በእንተ ሕማሙ ወሞቱ ወትስብእቱ ከመ ፍቁር ወሰብአ ቤቱ ወአኮ ከመ ነኪ ራን[፲፰] ::

፲፮ ሚል. ፬ - ፮
፲፯ . ማቴ. ፭ - ፲፯ - ፲፰
፲፰. ሉቃ. ፱- ፳፰ — ፴፩

፻፷፰፤እነሱን ትመስሉ ዘንድ እንለ ምናችኋለን፤ ቃላቸውንም ስሙ፤ ከቀድሞው ልማድም ራቁ ፤ ፊተ ኞች አልፈዋልና ::

፻፷፱፤እናንተም አዲሶችን ሁኑ፤ ሁሉ በእሱ የተፈጠረ ፤ ነፍሳትን የምትመልስ ነውር የሌለባት ያለ መለየት ያለ መጕደልና ያለ መለ ወጥ የእርሱን ስም በውስጥ ፍጹም ያደረግንባት የነፍሳችን መዳኛና ንጹሕ ሕግን የሰጠን ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስን አው ቃችሁታልና::

፻፸፤ ይህን ለረሱ ዕብራውያንም ይህን የጽድቅና የቅድስና ትእዛዝን ያዘዛችሁን የእግዚአብሔርን ሰው የሙሴን ሕግ አስቡ የሚል መታ ሰቢያን በነቢዩ በሚልክያስ ሰጣ ቸው::

፻፸፩፤ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም የኦሪትን ሕግ አልሻረም ፤ አላጓ ደለምም፤ ነገር ግን ይህ ሁሉ እስ ኪደረግ ድረስ ከኦሪት አንዲቱ ቃል አታልፍም አለ፤ ሁለተኛም እፈጽማቸው ዘንድ ነው እንጂ፤ ኦሪትንና ነቢያትን ላሳልፋቸው አልመጣሁም አለ ::

፻፸፪፤ ሕግን የሠራ ነቢይና ንጉሥ ሙሴ ፤ ቀናተኛው ነቢይ ኤልያስም በፊታቸው መልኩ በተ ለወጠ ጊዜ ከጌታ ጋር ታዩ ፤ ሰው ስለመሆኑ ስለ ሕማሙና ስለሞቱ ምስክር ሆኑ ፤ እንደ ወዳጅና እንደ ቤቱ ሰዎች እንጂ እንደ ባዕዶች አይደሉምና::





፻፸፫፤ወሀበ እግዚአብሔር ሥር ዐተ ፲ቱ ቃላት ዘውስተ ኦሪት ወነቢያት በቅዱሳን ወእሙንቱሰ ነበሩ እንዘ ይሰምዑ ቃሎ እምቅ ድመ ይግበሩ ሎሙ ጣዕዋ ላሕም ዘሰመይዎ ግብፃውያን ሀቤ[፲፱]::

፻፸፬፤ እስመ ሥርዐትሰ ጽድቅ ውእቱ::

፻፸፭፤ ወበእንተዝ ተሰምየ ሕገ ወይፌትሕ በርትዕ ::

፻፸፮፤ሲሞንሰ ወእለሂ ምስሌሁ ጸልኡ ዘንተ ሥርዐተ ወይዌድሱ ርእሶሙ ወእሙንቱሰ ይወርዱ ውስተ ገሃነም::

፻፸፯፤ሕግሰ ኄር ወቅዱስ ውእቱ እስመ ይቤ እመ ትፈቅድ ትግበር ሊተ ምሥዋዐ ሕንጽ ሊተ በም ድር ወኢይቤ ሕንጽ ሊተ ዘእንበለ ሥምረት ::

፻፸፰፤እስመ ይጽሕቅ እግዚአብ ሔር በኀቤነ መሥዋዕተ ወቍ ርባነ::

፻፸፱፤አቤልሰ ወኖኅ ወአብርሃም መሥዋዕተ ወዕጣነ አዕረጉ ኀቤሁ በፈቃዶሙ::

፻፹፤ወከማሁ በፈቃዶሙ ዕብራ ውያንሂ ገብሩ ዘንተ፤ወአኮ ውእቱ ዘአዘዞሙ ዳዕሙ ለሊሆሙ በሥ ምረቶሙ ውእቱሂ ተወክፈ መሥ ዋዕቶሙ ዘአዕረጉ ሎቱ በልብ ንጹሕ ::

፲፱ ዘፀ. ፳ - ፫ - ፲፰

፻፸፫፤ እግዚአብሔርም በኦሪትና በቅዱሳን ነቢያት ውስጥ ያሉ የአሥሩን ቃላት ሥርዐት ለሕ ዝቡ ሰጠ፤ እነርሱም ግብፃውያን አምላክ ያሉት የላም ጥጃን አስመ ስለው ጣዖትን ከመሥራት አስቀ ድመው ቃሉን ሲሰሙ ኖሩ::

፻፸፬፤ሥርዐት ጽድቅ ነውና ::

፻፸፭፤ ስለዚህም ሕግን ተባለ በእ ውነትም ይፈርዳል::

፻፸፮፤ሲሞንና ከርሱ ጋራ የነበሩ ግን ይህን ሥርዓት ጠሉ ፤ እራሳቸውንም ያመሰግናሉ ፤ እነ ርሱ ግን ወደ ገሃነም ይወርዳሉ ::

፻፸፯፤ ሕጉ ግን ቸርና ቅዱስ ነው፤ መሠዊያን ትሠራልኝ ዘንድ ብትወድ በምድር ሥራልኝ አለ እንጂ ያለ ፈቃድህ ሥራልኝ አላለምና::

፻፸፰፤እግዚአብሔር መሥዋዕት ንና ቍርባንን ከእኛ ይፈልጋልና::

፻፸፱፤ አቤልና ኖኅ አብርሃምም መሥዋዕትንና ዕጣንን በፈቃዳ ቸው ወደ እርሱ አሳርገዋልና::

፻፹፤እንዲሁ ዕብራውያንም በፈቃ ዳቸው ይህን አደረጉ፤ እርሱ ያዘዛ ቸው አይደለም ፤ እነርሱ በፈቃዳ ቸው ነው እንጂ ፤ እርሱም በን ጹሕ ልቡና ያሳረጉለትን ተቀበለ::

፻፵፩፡ወበእንተዝ ይቤ ኢይፈቅድ ዕጣነክሙ ወኢይጽሕቅ ወኢምንተኒ እስመ ዚአየ ውእቱ ኵሉ ዓለም ወኵሉ ዘውስተ ትካት መዋዕል ረሰዕዎ አሕዛብ ለእግዚአብሔር ወረሰዩ ሎሙ ጣዕዋ ላሕም አምላከ ህየንተ እግዚአብሐር ዘበአማን::

፻፵፩፡ስለዚህም እንዲህ አለ ፤ ዕጣናችሁን አልወድም ፤ ምንም አልሻም ፤ ዓለም ሁሉ የኔ ነውና በቀድሞ ዘመን የነበሩ ሰዎች ሁሉ እግዚአብሔርን ረሱት ፤ የላም ጥጃንም ስለ እውነተኛው እግዚአብሔር ፈንታ አምላክ አደረጉላቸው ::

፻፵፪፡ አመ ይወፅኡ እምግብፅ ይቤ አሮን እሉ እሙንቱ አማልክቲከ እስራኤል ዘአውፅኡከ እምድረ ግብፅ ወእሙንቱሰ አምለኩ ጣዕዋ ላሕም በዕልወት ወንደግዎ ለእግዚአብሐር ዘፈነወ ሙሴሃ ወአውፅኦሙ እምዕፁብ ኵነኔ ::

፻፵፪፡ከግብፅም በወጡ ጊዜ አሮን እስራኤል ሆይ ፤ ከግብፅ ምድር ያወጡህ አምላኮችህ እሊህ ናቸው አለ ፤ እነርሱም በክህደት የላም ጥጃን አመለኩ ፤ ሙሴን ልኮ ከሚያስጨንቅ አገዛዝ ያወጣቸው እግዚአብሔርን ተዉት ::

፻፵፫፡ ወናሁ ገብረ እግዚአብሔር ተአምራተ በእደ ሙሴ ገብሩ ወበትር ዘአማሰኖሙ ለግብፃውያን በ፲ቱ መቅሠፍት ዝንቱ ውእቱ፣ ወቦቱ ዘበጣ ለባሕረ ኤርትራ ወአኅለፎሙ እንተ ማዕከላ ከመ ምርዋጸ አፍራስ በውስተ የብስ ወለጸላእቱሰ አስጠሞሙ ውስቴታ::

፻፵፫፡ እግዚአብሔርም በወዳጁ በሙሴ እጅ ታምራትን አደረገ ፤ በበትሩም ግብፃውያንን በአሥር መቅሠፍት ያጠፋቸው እርሱ ነው፤ በዚያም በትር የኤርትራን ባሕር መትቶ በደረቅ እንዳለ ፈረስ መሮጫ አድርጎ በመካከሏ አሳለፋቸው ፤ ጠላቶቹንም በውስጧ አሰጠማቸው::

፻፵፬፡ወረሰየ ጥዑመ ነቅዐ ማይ መሪረ ወአንቅዐ ኰኵሐ ወአውሐዘ ሎሙ ማየ::

፻፵፬፡ መራራውን የውሃ ምንጭ ጣፋጭ አደረገ ፤ ጭንጫውንም ሰንጥቆ ውሃን አፈለቀላቸው ::



፻፵፭፡ወጸለሎሙ መዓልተ በደመና ወሌሊተ በዐምደ እሳት ወአብርሀ ሎሙ ወመርሐሙ ወእሙንቱሰ ኢያእመሩ ኀበ ይበጽሑ::

፻፵፭፡ ቀን በደመና ጋረዳቸው ፤ ሌሊትም በእሳት ምሰሶ እያበራ መራቸው ፤ እነርሱ ግን የሚደርሱበትን አያውቁም ነበር::

፻፵፮፡ ወአውረደ ሎሙ መና ይብልዑ እምሰማይ ወአዝነመ ሎሙ ሥጋ ከመ መሬት::

፻፵፮፡መናንም ይበሉ ዘንድ ከሰማይ አወረደላቸው ፤ ሥጋንም እንደ መሬት አዘነመላቸው::

፻፵፯፡ወወሀቦሙ ሕገ በገዳም ወረሰዮሙ ድልዋነ ይስምዑ ቃሎ ኀደግዎ ለዘገብረ ሎሙ ዘንተ ኵሎ ::

፻፵፯፡በምድረ በዳም ሕግን ሰጣቸው ፤ ቃሉንም ይሰሙ ዘንድ የተዘጋጁ አደረጋቸው ፤ ይህን ሁሉ ያደረገላቸውን ተዉት ::

፻፵፰፡ ወይቤልዎ ለአሮን ግበር ለነ አማልክተ እለ የሐውሩ ምስሌነ ወገብረ ሎሙ ጣዕዋ ላሕም ወሰገዱ ሎቱ::

፻፵፰፡አሮንንም ከኛ ጋራ የሚሄዱ አምላኮችን ሥራልን አሉት፤ እርሱም የላም ጥጃን ሠራላቸው ፤ እነርሱም ሰገዱለት::

፻፵፱፡ ወአእመረ እግዚአብሔር ከመ አልቦ አኰቴት በእንተ ኵሉ ዘገብረ ሎሙ ::

፻፵፱፡እግዚአብሔርም ስለ አደረገላቸው ሁሉ ምስጋና እንደሌለው ዐወቀ ::

፻፶፡ወእሙንቱሰ ተአስሩ በማእሰር ዘኢይትፈታሕ ወወድቁ ውስተ መሥገርት እንተ አልባቲ ሙጻአ ወምጉያይ::

፻፶፡እነርሱም በማይፈታ ማሠሪያ ታሥረው መውጫና መሸሻ በሌለባት ወጥመድ ውስጥ ወደቁ::

፻፶፩፡ ወአንትሙሰ ሶበ ትገብሩ ምሥዋዐ አዕርጉ ውስቴቱ ቍርባነ ኵሎ ጊዜ እስመ ውእቱ ይቤ ረሳዕኮ ለእግዚአብሔር ዘአድኀነከ ወአልብከ አኰቴተ ስምየ::

፻፶፩፡ እናንተ ግን መሠዊያን በሠራችሁ ጊዜ ሁሉ በውስጡ ቍርባንን አሳርጉ ፤ እርሱ ያዳነህ እግዚአብሔርን ረሳኸው ፤ ስሜን ማመስገንንም የለህም ብሏልና::

፻፶፪፤አብአ እንከ መባአክሙ ከመ ትዘከሩ አኰቴተ ስምየ በህየ ወኢ ትወልጡ እንስሳ ርኩሰ ህየንተ ንጹሕ::

፻፶፫፤ወእመሰ ኢገበርክሙ ከመዝ አመጽእ ላዕሌክሙ ዐቢየ መቅሠፍተ ከመ ገብር እኩይ ወሀካይ ወአብድ ወኢትትአሰሩ በማእሰረ ትእዛዝየ::

፻፶፬፤ ተዓቀቡ እንከ ወኢትደቁ ውስተ ስሕተተ ብዙኃን አማልክት ከመ ኢይርከብክሙ ቃል ዘይቤ አይቴ ውእቱ አማልክቲከ እስራኤል::

፻፶፭፤ ወተዘከሩ ዘጽሑፍ ዘይቤ ስማዕ እስራኤል እግዚአብሔር፣ አምላክከ፤ እግዚአብሔር አሐዱ ውእቱ[፳]::

፻፶፮፤አንትሙሰ ንበሩ በዛቲ ሥርዐት ወአእምሩ ከመ አልቦ ባዕድ አምላክ ዘእንበሌሁ በሰማይ ወበ ምድር::

፻፶፯፤አፍቅሮ ለእግዚአብሔር አምላክከ በኵሉ ልብከ ወበኵሉ ኃይልከ ወበኵሉ ሕሊናከ ወኢያሁ ባሕቲቶ ፍራህ ወኢትረሲ ውስተ ልብከ ስመ አማልክተ ነኪር ፣ ወኢትዝክሮሙ በአፉከ እስመ በእንተ ጽልሑተ ልቦሙ አእመ ሮሙ እግዚአብሔር::

፳፤ ዘዳግ ፮ — ፬ - ፮

፻፶፪፤እንግዲህም በዚያ ስሜን ማመስገንን ታስቡ ዘንድ መብዓ ችሁን አግቡ ፣ ስለ ንጹሑ ፈን ታም ርኩሱን እንስሳ አትለ ውጡ::

፻፶፫፤እንደዚህ ባታደርጉ ግን እንደ ክፉና ሐኬተኛ ፣ እንደ አላዋቂም ባሪያ ታላቅ መቅሠፍትን በናንተ ላይ አመጣለሁ ፣ በትእዛዜ ማሰ ሪያም አትታሰሩም::

፻፶፬፤እንግዴህ ተጠበቁ ፤ እስራ ኤል ሆይ አምላኮችህ ወዴት ናቸው የሚለው ቃል እንዳያገኛ ችሁ ፤ በብዙዎች ጣዖታት ስሕተ ትም አትውደቁ ::

፻፶፭፤እስራኤል ሆይ ! ስማ አምላክህ እግዚአብሔር አንድ እግዚአብሔር ነው ፣ ተብሎ የተ ጻፈውንም ቃል አስቡ::

፻፶፮፤ እናንተስ በዚች ሥርዐት ኑሩ ከእርሱም ሌላ በሰማይም በምድርም ሌላ አምላክ እንደሌለ ዕወቁ::

፻፶፯፤እስራኤል ሆይ ! በፍጹም ልብህ ፣ በፍጹም ኃይልህ ፣ በፍ ጹምም ሐሳብህ አምላክህ እግዚአ ብሔርን ውደደው ፣ እርሱንም ብቻ ፍራ ፣ በልብህም ውስጥ የተለየ የጣዖታትን ስም አታድ ርግ ፤ በአፍህም አትጥራቸው ፣ እግዚአብሔር ስለ ልባቸው ሽንገላ አውቆአቸዋልና::



፻፶፰፤ ወአንትሙሰ አእመርክምዎ ለ፩አምላክ በልብ ንጹሕ ወበሠናይ ሕሊና ወሰማዕክሙ ቃሎ ለመድኅን ብፁዓት አዕይንቲክሙ እለ ርእያ ወአእዛኒክሙ እለ ሰምዓ ::

፻፶፱፤ናሁ ፈትሐክሙ እማእሰር ወግዕዝክሙ እምግብርናት::

፻፷፤ወዓዲ ይቤ ኢይብለክሙ አግብርትየ እስመ ገብርሰ ኢየአ ምር ዘይሬስዮ እግዚኡ አላ ዳዕሙ አዕርክትየ አንትሙ ::

፻፷፩፤ ናሁ መሀርኩክሙ ኵሎ ዘሰማዕኩ በኀበ አቡየ[፳፩] ::

፻፷፪፤ወእለሰ ይፈቅዱ ኢይርአዩ ወኢይስምዑ ገዝፈ ልቦሙ ወር ኀቁ እምኔሁ::

፻፷፫፤አንትሙሰ ብፁዓን አንትሙ ዘሠዓረክሙ እግዚአብሔር እመር ገም እስመ ዘመጽአ ክርስቶስ ወልደ እግዚአብሔር አጽንዐ ሕገ ወፈጸመ ወአሰሰለ ክቡደ ጾረ ዘው ስቴቱ ፣ አድኀነነ ወአግዐዘነ እምተቀንዮ ለኃጢአት ወመሐረነ ወወሀበነ ሕይወተ ዘለዓለም ::

፳፩ ዮሐ. ፲፭ - ፲፭

፻፶፰፤እናንተ ግን አንዱን አምላክ በንጹሕ ልብና በበጎ አሳብ አውቃ ችሁታል፣የመድኀኒንም ቃል ሰም ታችኋል ፤ ያዩ ዓይኖቻችሁ ፣ የሰሙም ጆሮዎቻችሁ ብፁዓን ናቸው::

፻፶፱፤እነሆ ከማሰሪያ ፈታችሁ ፣ ከባርነትም ነፃ ወጣችሁ::

፻፷፤ዳግመኛም ባሮቼ አልላች ሁም አለ ፣ ባሪያ ጌታው የሚያ ደርገውን አያውቅምና ፣ ወዳጆቼ ናችሁ እንጂ::

፻፷፩፤እነሆ በአባቴ ዘንድ የሰማ ሁትን ሁሉ አስተማርኋችሁ::

፻፷፪፤ እንዳያዩ እንዳይሰሙ የሚ ወዱ ግን ልቡናቸው ደንድኖ ከርሱ ራቁ::

፻፷፫፤እግዚአብሔር ከርግማን የለ ያችሁ እናንተ ግን ንዑዳን ክቡራን ናችሁ ፤ የእግዚአብሔር ልጅ ክር ስቶስ ሕግን አጽንቷልና ፤ ሕጉ ንም ፈጽሞ ከእኛ ከባድ ሸክምን አርቋልና ፤ እኛንም አድኖ ከኃጢ አት መገዛት ነፃ አውጥቶናልና ፤ ይቅር ብሎም የዘለዓለም ሕይ ወትን ሰጥቶናልና::

፻፳፬፤ወካዕበ ይቤ ዘይፈቅድ ይት ልወኒ ይጽናሕ ዳግመ ምጽአትየ።

፻፳፭፤ ወውእቱሰ ኢተወክፈ መሥዋዕተ ወቍርባነ ዘያበውኡ አሕዛብ እስመ ብዙኀ ጊዜ አበሱ ሎቱ።

፻፳፮፤ ወለእሙንቱሰ ይመስሎሙ በአብዝኖ መሥዋዕት ዘይድኀኑ እመ ቅሠፈተ መዓቱ ለእግዚአብሔር ዘእንበለ ዳዕሙ ንሕነ ንስብሖ።

፻፳፯፤ወዓዲ ይቤ በእንተ ምንት ታመጽኡ ሊተ ዕጣነ እምሳባ ወቀ ናንሞሰ እምርኁቅ ብሔር ኢይ ሠምር መሥዋዕተክሙ ወኢ ይትዌከፍ ዕጣነክሙ።

፻፳፰፤ ወካዕበ ይቤ ኢሳይያስ ለም ንት ታበውኡ ሊተ መሥዋዕ ተክሙ ፤ ጽጉብ አነ እመሥዋዕተ ሐራጊት ወአልህምት ወስብሐ አባግዕ፤ ኢይፈቅድ ደመ ላህም ወጠሊ እመኒ አምጻእክሙ ኢታስ ተርእዩኒ መኑ ኃሠሦ ለዝንቱ እምእዴክሙ።

፻፳፱፤ኢትድግሙ እንከ ከይደ ዐፀደ ቤትየ ወእመኒ አምጻእክሙ ስንዳሌ ከንቱ ውእቱ ወዕጣንክሙ ርኩስ ፤ ወበዓላቲክሙ ወሰንበ ታቲክሙ ዕለተክሙ ኢይፈቅድ፤ ጾመክሙኒ ወጸሎተክሙኒ ኢይ ፈቅድ ፤ ጸልአት ነፍስየ ዘንተ ወሰቈራረ ኮንክሙኒ።

፻፳፬፤ሁለተኛም ሊከተለኝ የወ ደደ ሁለተኛ አመጣጤን ይጠብቅ አለ ።

፻፳፭፤እሱ አሕዛብ የሚአቀርቡ ትን መሥዋዕትንና ቍርባንን አልተቀበለም ፤ እሱን ብዙ ጊዜ በድለዋልና ።

፻፳፮፤ ለነሱ ግን ከእግዚአብሔር ከቁጣው መቅሠፍት መሥዋዕትን በማብዛት የሚድኑ ይመስላቸ ዋል፤ እኛ እናመስግነው እንጂ ።

፻፳፯፤ዳግመኛም መሥዋዕታችሁን አልወድም ፤ ዕጣናችሁንም አልቀ በልም ፤ ዕጣንን ከሳባ፣ ቀናንሞ ስንም ከሩቅ አገር ስለምን ታመ ጡልኛላችሁ አለ።

፻፳፰፤ ሁለተኛም ኢሳይያስ የላ ምና የፍየል ደምን አልወድም፤ ብታመጡም አታሳዩኝ ፤ ይህን ከእጃችሁ ማን ፈለገው? የበጎችን ስብ የላሞችንና የጊደሮችን መሥ ዋዕት እኔ ጠግቤያለሁ መሥዋዕ ታችሁን ለኔ ለምን ታቀርባላችሁ? አለ ።

፻፳፱፤እንግዲህ የቤቴን ቦታ መርገ ጥንም አትድገሙ ፤ ስንዴንም ብታመጡ ከንቱ ነው ፤ ዕጣናች ሁም የረከሰ ነው ፤ ሰንበቶቻችሁ ንም ፤ በዓሎቻችሁንም ቀናች ሁንም አልፈቅድም ፤ ጸሎታ ችሁንና ጾማችሁንም አልሻም ፤ ሰውነቴ ይህን ጠልታ አስጸያፊ ሆናችሁብኝ ።



፻፴፤ወዓዲ ይቤ ነቢይ አእትት እምኔየ ድምፀ መዓትከ።

፻፴፩፤ወካዕበ ይቤሎ ሳሙኤል ነቢይ ለሳኦል ሶበ ይፈቅድ ይሡዕ ይኄይስ ሰሚዕ እምሠዊዕ ወተአ ዝዞ እምስብሐ አባግዕ እስመ ኢይፈቅድ እግዚአብሔር ትሡዕ ሎቱ ዘእንበለ ዳዕሙ ትስማዕ ቃሎ።

፻፴፪፤ወዳዊትኒ ይቤ ኢይነሥእ አልህምተ እምቤትከ ወኢሐራጊተ እመርዔትከ እስመ ዚአየ ውእቱ ኵሉ አራዊት ዘገዳም እንስሳ ገዳ ምኒ ወአልህምት ወአአምር ኵሎ አዕዋፈ ሰማይ ወስነ ገዳምኒ ኀቤየ ሀሎ እመኒ ርኅብኩ ኢይስእለከ እስመ ዚአየ ውእቱ ኵሉ ዓለም በምልዑ ኢይበልዕ ሥጋ ላህም ወኢይሰቲ ደመ ጠሊ[፳፱] ሡዕ ለእግዚአብሔር መሥዋዕተ ስብ ሐት ወፈኑ ለልዑል ጸሎተከ ።

፻፴፫፤ ወዓዲ ጽሑፍ ውስተ መጽሐፍ ከመ ውእቱ ኢይፈቅድ ዕጣነ እለ አበሱ ሎቱ ፤ እስመ ርኩስ በኀቤሁ መሥዋዕቶሙ ለዕ ልዋን እለ ያበውኡ ዘእንበለ ሕግ ወኵሉ ዘይበልዕ እምኔሁ ይረ ኵስ ።

፳፱ መዝ. ፵፱ - ፱ - ፲

፻፴፤ዳግመኛም ነቢይ የቍጣህን ድምጽ ከኔ አርቅ አለ።

፻፴፩፤ሁለተኛም ሳሙኤል ሳኦልን መሥዋዕትን ይሠዋ ዘንድ ቢወድ ከመሥዋዕት መስማት፣ ከበጎች ስብም መታዘዝ ይሻላል፣ እግዚ አብሔር ቃሉን ትሰማ ዘንድ እንጂ መሥዋዕትን ልትሠዋለት አይፈቅድም እና አለ ።

፻፴፪፤ ዳዊትም ከቤትህ ላሞችን፣ ከመንጋዎችህም ጊደሮችን አል ቀበልህም፣ የምድረ በዳ አራዊት ሁሉ የኔ ናቸውና ፤ ላሞችና የም ድረበዳ እንስሳም የሰማይ ወፎች ንም ሁሉ ዐውቃለሁና፣የምድረ በዳ ጌጥም በኔ ዘንድ አለና፣ ብራብም አለምንህም ፤ ዓለም ሁሉ በሞላ የኔ ነውና፣ የላም ሥጋን አልበላም ፤ የፍየል ደም ንም አልጠጣም ፤ ለእግዚአብሔር የምስጋና መሥዋዕትን ሠዋ፣ጸ ሎትህንም ለልዑል ስጥ እንጂ አለ ።

፻፴፫፤ ዳግመኛም እሱን የበደሉ ሰዎች ዕጣንን እሱ እንዳይወድ በመጽሐፍ ውስጥ የተጻፈ ነው፣ ያለ ሥርዓት የሚያቀርቡት የከሃ ዲዎች መሥዋዕት በእሱ ዘንድ ርኩስ ነውና ፤ ከመሥዋዕቱም የሚበላ ይረክሳል።

፻፹፬፡ ወውእቱ ይፈቅድ ፈድፋደ ልበ የዋሀ ወመንፈሰ ትሑተ ዘይኄይስ እመሥዋዕት።

፻፹፭፡ናሁ እንከ መጽአ ያዕርዕ እሰ ያበውኡ መሥዋዕተ ደም ፤ እስመ ውእቱ ነገረ በኦሪት ከመ እግዚአብሔር አምላክ አሐዱ ውእቱ[፳፫] ።

፻፹፮፡ወካዕበ ይቤ በወንጌል ዛቲ ይእቲ ሕይወት ዘለዓለም ከመ ያዕምሩከ ለከ ለ፩ ዘበአማን አምላክ[፳፬]።

፻፹፯፡ወዓዲ ይቤ አፍቅር ቢፀከ ከመ ነፍስከ ፤ ወዳግመ ይቤ አፍቀርኩክሙ መፍትው ትትፋቀሩ በበይናቲክሙ ከመ አነ አፍቀርኩክሙ[፳፭]።

፻፹፰፡እስመ ከመዝ ይቤ መጽሐፍ ኢትቅትል ነፍሰ፤ ወውእቱሰ አዘዘ ግሙራ ኢንጽላእ መነሂ ዘይቤ ናሁ አዘዘ ኢይዘምዉ ወኢይፍትዉ ብእሲተ ባዕድ።

፻፹፱፡ ይቤ ኢትስርቅ ወውእቱ አዘዘ ንትገሃሥ እምኵሉ ምግባር እኩይ ወናፍቅር ጸላዕተነ[፳፮] እስመ ዘይቤ ኢትፍድዩ እኩየ ለዘአሕሠመ ላዕሌክሙ አዘዘነ ንግበር ሰላመ ምስለ ኵሉ ፤ እስመ ምሕረት ይኄይስ እምእለ ይፈቅዱ በቀለ በእኩይ።

፳፫ ዘዳግ. ፮ — ፰
፳፬ ዮሐ ፲፯ - ፫
፳፭ ማቴ. ፳፪ -፴፱
፳፮፥ ዮሐ. ፲፫ - ፴፬

፻፹፬፡እሱም ከመሥዋዕት የሚሻል ቅን ልቡናና ትሑት ሰውነትን ፈጽሞ ይወዳል ።

፻፹፭፡እንሆ የደም መሥዋዕትን የሚአቀርቡትን ያስቀር ዘንድ መጣ ፤ እሱ በኦሪት ፈጣሪ እግዚአብሔር አንድ እንደሆነ ተናግሯልና።

፻፹፮፡ሁለተኛም በወንጌል በእውነት አንድ አምላክ የምትሆን አንተን ያውቁህ ዘንድ የዘለዓለም ሕይወት ይህች ናት አለ ።

፻፹፯፡ዳግመኛም ባልንጀራህን እንደራስህ አድርገህ ውደድ አለ ፤ ሁለተኛም እኔ ወደድኋችሁ አለ ፤ እኔ እንደ ወደድኳችሁ እናንተም እርስ በርሳችሁ ትዋደዱ ዘንድ ይገባል።

፻፹፰፡መጽሐፍ እንዲህ ብሏልና ነፍስን አትግደል ፤ እርሱስ ማንንም ፈጽመን እንዳንጠላ አዘዘ ፤ እነሆ እንዳይሰስኑ አዘዘ ያለው የሌላውን ምሽት ፈጽመው እንዳይመኙ ነው።

፻፹፱፡አትስረቅ አለ ፤ እርሱ ግን ከክፉ ሥራ ሁሉ እንርቅና ጠላቶቻችንንም እንወድ ዘንድ አዘዘ ፤ በናንተ ላይ ክፋትን ለሠራ ሰው ክፉን አትመልሱለት ፤ ስለ አለውም ከሁሉ ሰላምን እናደርግ ዘንድ አዘዘን ፤ በክፋት መበቀልን ከሚወዱ ይልቅ ይቅርታ ይሻላልና ።



፻፺፡ይቤ አክብሩ አበዊክሙ ወውእቱሰ አዘዘነ ናትሕት ርእሰነ ለኵሉ፤ አጽርዐ ግዝረተነ ወለሊሁ ፈጸመ ግዝረተ ወውእቱሰ ፈጸመ ተስፋ ዘይሴፈዎ ኵሉ ዓለም።

፻፺፩፡ ዘይቤ አግብእ መሐላከ ለእግዚአብሔር አዘዘነ ኢንምሐል ወኢበምንትኒ።

፻፺፪፡ህየንተ መሥዋዕት ዘደም ወሀበነ ቍርባነ ነባቢተ ዘእንበለ ደም ።

፻፺፫፡ ወህየንተ መሥዋዕት ዘ፩ መካን አዘዘነ ይኩን ቍርባን ውስተ ኵሉ ምድር እምሥራቀ ፀሐይ እስከነ ዓረብ።

፻፺፬፡ ወለክህነቱ ይቤ ሙሴ በውስተ ሕግ ፤ ንብብ ቃለ ዘአዘዝኩከ እንዘ ትነብር አው እንዘ ትቀውም ወእመኒ እንዘ ተሐውር ውስተ ፍኖት ።

፻፺፭፡ ወዳዊትኒ ይቤ ዘዳዕሙ ሕገ እግዚአብሔር ሥምረቱ ወዘሕጎ ያነብብ መዓልተ ወሌሊተ[፳፯] ወበኵለሄ አዘዘ ይግበሩ በውስተ ሕግ ወኢይዕልዉ ሥርዐተ።

፻፺፮፡ወካዕበ ይቤ ብፁዓን እለ ንጹሐን በፍኖቶሙ ወእለ የሐውሩ በፍናዊሁ ወበኵሉ ልቦሙ የኀሥሥዎ[፳፰]።

፳፯ መዝ. ፩ — ፩ — ፪ ፤ ፻፲፰ ፩ - ፪

፻፺፡አባቶቻችሁን አክብሩ አለ ፤ እርሱ ግን ለሁሉ እራሳችንን እናዋርድ ዘንድ አዘዘን ፤ ግዝረታችነን አስቀረ ፤ እርሱ ግን ግዝረትን ፈጸመ ፤ ዓለም ሁሉ የሚመኘው ተስፋን ፈጸመ ።

፻፺፩፡ መሐላህን ወደ እግዚአብሔር መልስ ያለ እርሱ በምንም ፈጽመን እንዳንምል አዘዘን።

፻፺፪፡ስለ ደም መሥዋዕት ፈንታ ያለ ደም የምትናገር ቍርባንን ሰጠን ።

፻፺፫፡ በአንድ ቦታ ስለ ምትደረግ መሥዋዕት ፈንታም ፤ ቍርባን ከፀሐይ መውጫ እስከ ፀሐይ መግቢያ ድረስ በምድር ሁሉ ይደረግ ዘንድ አዘዘን።

፻፺፬፡ሙሴም ለክህነቱ በመጽሐፍ ውስጥ፤ ስትቀመጥ ወይም ስትቆም ፤ ወደ ጐዳና ስትሔድም ያዘዝኩህን ቃል ተናገር አለ።

፻፺፭፡ ዳዊትም የእግዚአብሔር ሕግ ፈቃዱ የምትሆን ሌሊቱን፤ ቀኑንም፤ ሕጉን የሚያነብብ ብፁዕ ነው አለ፤ሁለጊዜም በመጽሐፍ ያለውን ይሠሩ ዘንድ ሥራትንም እንዳያፈርሱ አዘዘ።

፻፺፮፡ዳግመኛም አለ በጐዳናቸው ንጹሐን የሆኑ ሰዎች ፤ በመንገዶቹም የሚሄዱ በፍጹም ልቡናቸውም የሚፈልጉት ሰዎች ብፁዓን ናቸው ።

፻፹፯፤ወዓዲ ይቤ በወንጌል ብፁዓን አንትሙ እመ ገበርክምዎ ለዝንቱ እስመ በእንተዝ ይፌቅድ ይኩን ሕግ ገሃደ በጽድቅ ወያበርህ ለኵሉ ዓለም ለእለ የአምኑ በእግዚእነ ወኀደጉ አምልኮተ ጣዖት ወርኀቁ እምዐመፃ ወተወክፉ ቃሎ ሠናያተ::

፻፹፰፤ወለእለሂ መነኑ ኪዳናተ አይሁድ እለ ፆረ ልቦሙ ወተለዉ ፍኖቶሙ እለ ይቤሉ አልብነ ንጉሥ ዘእንበለ ቄሣር::

፻፹፱፤ወካዕበ ይቤሉ እመኀደግናሁ ለዝንቱ ይመጽኡ ሰብአ ሮሜ ወይነሥኡ ሕዝበነ ወብሔረነ ፤ ተነበዩ ላዕሌሁ::

፻፺፤ወይቤሉ ይኄይሰነ ንቅትል ፩ደ ብእሴ እምይትሀጐል ኵሉ ሕዝብ[፳፰] ::

፻፺፩፤አምኑ ቦቱ ኵሎሙ አሕዛብ ወነሥኡ ሮሜ ሢመቶሙ ወነሥኡ ኵሎ ሥርዐቶሙ::

፻፺፪፤ ወበእንተዝ ኮኑ ርጉማነ እስመ ኢክህሉ ገቢረ ትእዛዙ ::

፻፺፫፤ ወዓዲ ይቤ ርጉም ውእቱ ዘኢይገብር ኵሎ ትእዛዘ ዘጽሑፍ ውስተ መጽሐፈ ሕግ::

፳፰ ዮሐ. ፲፩ - ፶

፻፹፯፤ዳግመኛም በወንጌል ይህን ብታደርጉ ብፁዓን ናችሁ አለ ፤ ስለዚህም ሕግ በእውነት የተገለጠ ይሆን ዘንድ ይወዳል ፤ ጣዖት ማምለክን ትተው ፤ ከበደልም ርቀው በጎ ቃሎችንም ተቀብለው ፤ በጌታችን ሳመኑ ሰዎች በዓለም ሁሉ ያበራል ::

፻፹፰፤ ልባቸው የታወረ አይሁድ ንና ከቄሳር በቀር ንጉሥ የለንም የሚሉትን መንገድ የተከተሉትን መሐላ ለናቁ ያበራል ::

፻፹፱፤ ሁለተኛም ይህን ብንተወው የሮሜ ሰዎች መጥተው ሕዝባችንንና ሀገራችነን ይወስዳሉ ብለው በእርሱ ላይ ተናገሩ::

፻፺፤እንዲህም አሉ ፤ ሕዝቡ ሁሉ ከሚጠፋ አንድ ሰውን ብንገድል ይሻለናል ::

፻፺፩፤አሕዛብም ሁሉ አመኑበት ፤ የሮም ሰዎችም ሹመታቸውን ወሰዱ ፤ ሥርዓታቸውንም እጅ አደረጉ::

፻፺፪፤ ስለዚህም የተረገሙ ሆኑ ፤ ትእዛዙን ማድረግ አልቻሉምና ::

፻፺፫፤ ዳግመኛም አለ ፤ በሕግ መጽሐፍ የተጻፈውን ትእዛዝ ሁሉ የማይሠራ ርጉም ነው::



፻፺፬፤ ወንሕነሰ ንትሉ ፍኖቶ ለክርስቶስ ከመ ንርከብ በረከተ ወንትወከፍ ሕገ ወነቢያተ ወወንጌለ ቅዱሰ ወንትገኀሥ እምእለ ያመልኩ አማልክተ ብዙኃነ ወንርኀቅ እምቀታልያነ ክርስቶስ ወቀተልተ ነቢያት እሉ እሙንቱ አይሁድ መናፍቃን::

፻፺፭፤ወንሕነሰ ንተሐት ወንጽናዕ በአሚን በኢየሱስ ክርስቶስ ንጉሥ ዘቦቱ ሥልጣን ላዕለ ኵሉ ወውእቱ መምህረ ሕግ ወዐቃቤ ሥርዐት ::

፻፺፮፤ ረኀቁ እንከ እምፍልጠተ ኤጲስ ቆጰሳት ወካህናት ወሕዝብ እለ ያረኵሱ ኦሪተ ወነቢያተ ጸላእቱ ለእግዚአብሔር አኃዜ ኵሉ::

፻፺፯፤ወእለሰ የአምኑ በክርስቶስ ወልደ እግዚአብሔር ወይፈልጡ ልደቶ በሥጋ ፤ ወይፀርፉ ዲበ ሕማማቲሁ በሥጋ፤ ወይጼዕልዎ በመስቀሉ ወይሣለቁ በሞቱ ወኢየአምኑ ትንሣኤሁ ፤ ወያበጥሉ ልደቶ እምአብ እምቅድመ ኵሉ ፍጥረት፤ወይብሉ እሙንቱ ሥጋ ወነፍስ ውእቱ ወአልቦ መለኮት::

፻፺፰፤ወቦ ዘይቤሉ ከመ ኢየሱስ ክርስቶስ መልዕልተ ኵሉ ወይዌድስዎ ::

፻፺፱፤ወይብልዎ ባሕቲቱ ውእቱ አብ ወካዕበ ይቤሉ ውእቱ ወልድ ወጰራቅሊጦስ ኢሀለዉ ፤ እሉኬ ርኩሳን እምኵሉ ::

፻፺፬፤ እኛ ግን የክርስቶስን መንገድ እንከተል ፤ በረከትን እናገኝ ዘንድ ነቢያትንና ኦሪትን ቅዱስ ወንጌልንም እንቀበል፤ብዙ አማልክትን ከሚያመልኩ ሰዎችም እንለይ ፤ ከክርስቶስ ገዳዮችና ከነቢያት ገዳዮች እንራቅ ፤ እነዚህም መናፍቃን አይሁድ ናቸው::

፻፺፭፤ እኛ ግን ራሳችንን ዝቅ እናድርግ ፤ በሁሉ ላይ ሥልጣን ባለው በንጉሥ ኢየሱስ ክርስቶስ በማመንም እንጽና ፤ እርሱ የሕግ መምህርና የሥርዐት ጠባቂ ነውና ::

፻፺፮፤ ከኤጲስ ቆጶሳትና ከካህናት ከመለየት ራቁ፤ ኦሪትን ነቢያትን የሚያረክሱ ሕዝብ ሁሉን የፈጠረ የእግዚአብሔር ጠላቶች ናቸው::

፻፺፯፤በእግዚአብሔር ልጅ በክርስቶስ ስም የሚያምኑ በሥጋ መወለዱን ግን የሚለዩ ፤ በሥጋ በተቀበላቸው መከራዎቹም ላይ የሚዘብቱ ፤ በመስቀሉም የሚሳደቡ ፤ በሞቱም የሚሳለቁ ፤ ትንሣኤውንም የማያ ምኑ ፤ ከፍጥረቱም አስቀድሞ ከአብ መወለዱን የሚያፈርሱ አሉ ፤ ነፍስና ሥጋ ነው እንጂ፤መለኮት የለውም ይላሉ::

፻፺፰፤ ኢየሱስ ክርስቶስም ከሁሉ በላይ ነው ብለው የሚያመሰግኑት አሉ ::

፻፺፱፤ አብ ብቻ ነው የሚሉም አሉ ፤ ሁለተኛም እርሱ ወልድና ጰራቅሊጦስ የሉም የሚሉም አሉ፤ እሊህም ከሁሉ ይልቅ ርኩሳን ናቸው::

፪፻፥ወቦ እለ ይቤሉ ከመ ትንሣኤ ሙታን በነፍስ እለ እንበለ ሥጋ፤ ወለእሉ ይብሎሙ ሑሩ ውስተ እሳት ዘለዓለም::

፪፻፩፥ረኃቁ ኦ ፍቁራንየ አኀው እምእሉ ከመ ኢትትኰነኑ ኅቡረ ምስሌሆሙ::

፪፻፪፥ወእለሂ ይሬእዩ ኮከበ ወያመ ልኩ ኃይለ ሰማይ ወይትዓቀቡ ዕለተ ወሰዓታተ ለእሉ እንከ ይትዌከፍኑ ጸሎቶሙ ወይሠምርኑ ቍርባኖሙ ወይሰምዕኑ መጻሕፍቶሙ ቅዱሳተ::

፪፻፫፥እሉኬ ኮኑ መዝበረ እመንፈስ ቅዱስ ዘህልው ውስተ ልበ መሃይምናን::

፪፻፬፥ወይቤ ሰሎሞን በእንተ ቅዱሳን ይኩኑ ድልዋነ እመኒ ኖሙ ይትዓቀቡ ወእመኒ ነቅሑ ይጠበቡ በጽድቅ ወተፋቅሮ እስመ ኢይርኅቅ መንፈስ ቅዱስ እመሃይምናን ሕዝበ ክርስቲያን እምዕለተ ልደቶሙ እስከ አመ ይመውቱ ::

፪፻፭፥ወብእሲትኒ ዘትነብር ሰቡዐ መዋዕለ በደም ወእምድኅረ ወለደት ሐለየት በልባ ወትቤ እፎ የኀድር መንፈስ ቅዱስ ላዕሌየ እንዘ ርኵስት አነ፤ወእመሰ ውኅደ ሃይማኖት ወአልባቲ ምግባረ ሠናይ ኢየኀድር ላዕሌሃ መንፈስ ቅዱስ ::

፪፻፥ የሙታን ትንሣኤም ያለ ሥጋ በነፍስ ነው የሚሉም አሉ፤ እርሱም ወደ ዘለዓለም እሳት ሒዱ ይላቸዋል ::

፪፻፩፥ የተወደዳችሁ ወንድሞች ሆይ ! ከእነርሱ ጋር በአንድነት እንዳይፈረድባችሁ ከእነዚህ ራቁ::

፪፻፪፥ ኮከብን አይተው የሚያመልኩ፤የሰማይንም ጽናት የሚያመልኩ ፤ ዕለትንና ሰዓታትንም የሚጠባበቁ ፤ እንግዲህ የሊህን ጸሎት ይቀበላልን ፤ ቍርባናቸውንስ ይወዳልን ፤ ቅዱሳት መጻሕፍቶቻቸውንስ ይሰማልን::

፪፻፫፥ እሊህስ በምእመናን ልቡና ውስጥ ከሚኖር ከመንፈስ ቅዱስ ባዶ ሆኑ ::

፪፻፬፥ ሰሎሞንም ስለ ቅዱሳን እንዲህ አለ ፤ ቢተኙ ይጠበቁ ዘንድ፤ ቢነቁም በጽድቅና በፍቅር ይራቀቁ ዘንድ የተዘጋጁ ይሁኑ፤ ከተወለዱ ጀምሮ እስኪሞቱ ድረስ መንፈስ ቅዱስ ከክርስቲያን ወገኖች ከምእመናን አይርቅምና::

፪፻፭፥ ሴትም ከወለደች በኋላ በደም ፯ ቀን የምትቀመጥ፤እኔ ርኩስ ስሆን መንፈስ ቅዱስ፤ በኔ ላይ እንዴት ያድራል? ብላ በልቧ ብታስብ (ብትጠራጠር) ሃይማኖትም የጐደለባት በጎ ሥራም የሌላት ብትሆን መንፈስ ቅዱስ በላይዋ አያድርም::



፪፻፮፥እስመ ዝንቱ ግብር ኢኮነ ውጹዐ እምሕግ ወሰብሳብሰ ወደም ዘይለምዳ አንስት ወሕልም ኢይከልዕ መንፈስ ቅዱሰ ::

፪፻፯፥አላ ዳዕሙ ለዕልዋን መናፍቃን እለ ዐለዉ ሕገ ወሥርዐተ ኢየኃድር መንፈስ ቅዱስ ላዕሌሆሙ ::

፪፻፰፥ ወእለሰ አምኑ ወይሴፈዉ ዳግመ ምጽአቶ ለክርስቶስ የኀድር ላዕሌሆሙ መንፈስ ቅዱስ::

፪፻፱፥ ወእለሰ መንፈስ ቅዱስ አልቦሙ ይከውኑ ማኅደረ ለአጋንንት ርኩሳን ፤ እስመ ጸራቅሊጦስ ይጸልእ ሐሰተ ወኵሎ ምግባረ እኩየ፤ ወዲያብሎስ ይጸልእ ምግባረ ጽድቅ ወምግባረ ሠናይ ::

፪፻፲፥ወኵሉ ዘይጠመቅ በአሚን ይትፈለጥ እመንፈሰ ሰይጣን ወይከውን ማኅደረ ለመንፈስ ቅዱስ ወለዘሰ ይገብር ሥምረቶ ይመልዕ ላዕሌሁ ጥበብ ወአእምሮ ወኢይክል ቀሪበ ኀቤሁ መንፈስ ርኩስ::

፪፻፲፩፥ወመንፈስ ርኩስ ያፈቅር እለ አልቦሙ አኰቴት ሀካያነ ወኃጥአነ ወመሠርያነ እስመ ዲያብሎስ በሕፀተ አኰቴት ወድቀ እመንበሩ ወኮነ ዕሩቀ እምስብሐተ እግዚአብሔር፤ወለሊሁ ኀረየ ከዊነ ሰይጣን እምይኩን ሊቀ መላእክት ::

፪፻፮፥ ይህ ሥራ ከሕግ የወጣ አይደለምና ፤ ነገር ግን ጋብቻ የሴቶች ልማድና ደም ሕልምም መንፈስ ቅዱስን አይከለክልም ::

፪፻፯፥ነገር ግን ሕግንና ሥርዓትን በለወጡ በመናፍቃንና በከሃዲዎች ላይ መንፈስ ቅዱስ አያድርም እንጂ::

፪፻፰፥ በሚያምኑና የክርስቶስን ዳግም ምጽአት ተስፋ በአደረጉ ሰዎች ላይ ግን መንፈስ ቅዱስ ያድራል ::

፪፻፱፥መንፈስ ቅዱስ የሌለባቸው ሰዎች ለርኩሳን አጋንንት ማደሪያ ይሆናሉ ፤ መንፈስ ቅዱስ ሐሰትንና ክፉ ሥራን ሁሉ ይጠላልና፤ ዲያብሎስም የጽድቅ ሥራንና መልካም ሥራን ይጠላል::

፪፻፲፥በሃይማኖት የሚጠመቅ ሁሉ ከሰይጣን መንፈስ ይለያል ፤ ለመንፈስ ቅዱስም ማደሪያ ይሆናል፤ ፈቃዱን ለሚያአደርግም ዕውቀትና ጥበብ በላዩ ይመላል ፤ ርኩስ መንፈስም ወደ እርሱ መቅረብን አይችልም::

፪፻፲፩፥መንፈስ ርኩስም ምስጋና የሌላቸው ሰነፎችን ኃጢአተኞችንና ሥራየኞችን ይወዳል ፤ ዲያብሎስ ምስጋናን በማጕደል ከዙፋኑ ወድቋልና ፤ ከእግዚአብሔርም ምስጋና ባዶውን ቀርቷልና ፤ እርሱ ራሱ የመላእክት አለቃ ከመሆን ይልቅ ሰይጣን መሆንን መረጠ::

፪፻፲፪፤ወበእንተዝ መፍትው ለአን
ስት ይትዓቀባ እምኵሉ ነገር
እኩይ ወከንቱ ፣ ወይዘከራሁ ለእ
ግዚአብሔር ዘፈጠረ ኵሎ ወይት
ልዋ ሕጎ ወኢይግበራ ፍትወተ
ሥጋ ዘእንበለ በርቱዕ ሰብሳብ።

፪፻፲፫፤ ተዐቀቡ እምክረ እኩያን
ሰብእ ወእምትድምርቶሙ።

፪፻፲፬፤ወበእንተዝ ተገኀሡ ኦ ፍቁ
ራን አኃው እምኵሎሙ አረማው
ያን ዘይገብሩ እኩየ ወረሐቁ እም
ኔሆሙ ወኢታስቄርሩ ሥጋ
አብድንተ ሰብእ፤

፪፻፲፭፤ ነአምን ከመ የሐይዉ
ወይትነሥኡ ሙታን ዳግመ ።

፪፻፲፮፤ወከማሁ ኢኮነ ሰቈራረ ሰብ
ሳብ ዘበሕግ እስመ ትድምርተ
ብእሲ ወብእሲት ርቱዕ ዘፈጠረ
እግዚአብሔር ብእሴ ወብእሲተ
ወባረኮሙ ወይቤሎሙ ብዝኁ
ወተባዝኁ ወምልዕዋ ለምድር[፳፱]።

፪፻፲፯፤ናሁ ለበውነ ከመ እም
እግዚአብሔር ዝኵሉ ወዘእንበሌ
ሁሰ አልቦ ዘኮነ ወኢምንትኒ
እስመ ሰብአ ሰዶም ስሕቱ ወወ
ለጡ ፍጥረተ ወገብሩ ግብረ
ገሞራ።

፪፻፲፰፤ ወከማሁ እለ የሐውሩ
ምስለ እንስሳ ዝውእቱ ርኵስ
ወዕለወተ ሕግ ውእቱ[፴] ።

፪፻፲፪፤ ስለዚህም ለሴቶች ከከን
ቱና ከክፉ ነገር ሁሉ ተጠብቀው
ሁሉን የፈጠረ እግዚአብሔርን
ያስቡት ዘንድ ሕጉንም ይከተሉ
ዘንድ አገባብ ነው፣ ከሚገባ ኃብቻ
በቀርም የሥጋ ፈቃድን አይ
ሥሩ።

፪፻፲፫፤ከክፉ ሰዎች ምክር ከእነር
ሱም ኃራ አንድ ከመሆን ተጠ
በቁ።

፪፻፲፬፤ ስለዚህም የተወደዳችሁ
ወንድሞች ሆይ!ክፉን ከሚያደርጉ
አረማውያን ሁሉ ተለዩ ፣ ከእነር
ሱም ራቁ፣ የሞቱ ሰዎች ሰውነት
ንም አትጸየፉ።

፪፻፲፭፤ ሙታን ሕያዋን ሁነው
ዳግመኛ እንደሚነሱ እናምናለን።

፪፻፲፮፤እንዲሁም በሕግ የሚደረግ
ኃብቻ የሚያጸይፍ አይሆንም ፣
የወንድና የሴት አንድ መሆን
የሚገባ ነውና ፣ ወንድና ሴትን
የፈጠረ እግዚአብሔር ብዙ ፣
ተባዙ ፣ ምድርንም ሙሏት ብሎ
የባረካቸው ነውና ።

፪፻፲፯፤ እነሆ ይህ ሁሉ ከእግ
ዚአብሔር እንደሆነ ያለ እርሱም
ምንም የሆነ እንደሌለ አስተዋ
ልን ፣ የሰዶም ሰዎች ግን ሳቱ
ተፈጥሮንም ለውጠው የገሞራን
ሥራ ሠሩ ።

፪፻፲፰፤እንደዚሁም ወደ እንስሳ
የሚሔዱ አሉ፣ ይህም ርኵሰትና
ሕግን ማፍረስ ነው ።

፳፱ ዘፍ. ፩፥ ፳፯ — ፳፱
፴ ዘዳግ. ፳፯ — ፲፱



፪፻፲፱፤ ወእለሰ ይገብሩ ከመዝ
ኢያመስጡ እመቅሠፍት እስመ
አርኰሱ ሰብሳበ ንጹሐ ወገብሩ
ዘኢይደሉ ወዘሂ ኢእዙዝ ውስተ
ሕግ ።

፪፻፳፤ወይቤ ገብኡ በበይናቲሆሙ
ብእሲ ላዕለ ብእሲ ኃሣሮሙ
ገብሩ ወይገብእ ጌጋዮሙ ዲበ
ርእሶሙ ።

፪፻፳፩፤ እስመ ይቤ መጽሐፍ ለእ
መቦ ዘሰከበ ምስለ ተባዕት ከመ
ዘምስለ አንስት ርኵሰ ገብሩ
፪ሆሙ ሞተ ለይሙቱ[፴፩]።

፪፻፳፪፤ ወዘሰ ሰከበ ምስለ እንስሳ
ሞተ ለይሙት[፴፪] ወእመሰቦ
ዘዘመወ በብእሲተ ካልዑ ሞተ
ለይሙት እስመ ኀፍረት ለእስራ
ኤል።

፪፻፳፫፤ ዐስበ ደነሰ ዘማ ወቤዛ
ከልብ ኢያብኡ ውስተ ቤተ እግዚ
አብሔር ዝንቱ ውእቱ ዘኢእዙዝ
ውስተ ሕግ[፴፫]።

፪፻፳፬፤ ወሰብሳብ ንጹሕ ወባረኮ
እግዚአብሔር ለትድምርተ ብእሲ
ወብእሲት[፴፬]።

፪፻፳፭፤ወሰሎሞንሂ ይቤ ትድም
ርተ ብእሲ ወብእሲ ምኑን ውእቱ
በኀበ እግዚአብሔር።

፪፻፲፱፤ እንደዚህም የሚያደርጉ
ሰዎች ከመቅሠፍት አያመል
ጡም ፣ ንጹሕ ኃብቻን አርክሰ
ዋልና ፣ የማይገባውንና በመጽ
ሐፍ ያልታዘዘውን ሠርተዋልና።

፪፻፳፤ እንዲህም አለ ፣ ወንድ
በወንድ ላይ እርስ በርሳቸው
ተመላለሱ ፣ ውርደታቸውን አደ
ረጉ ፣ በደላቸውም በራሳቸው
ላይ ይመለሳል።

፪፻፳፩፤መጽሐፍ እንዲህ ብሏልና
ከሴቶች ኃራ እንደሚተኛ ከወንድ
ኃራ የተኛ ቢኖር ሁለቱም ርኵሰ
ትን አድርገዋልና ሞትን
ይሙቱ ።

፪፻፳፪፤ ከእንስሳ ጋር የተኛም
ሞትን ይሙት፣ በባልንጀራውም
ሚስት የሰሰነ ቢኖር ሞትን
ይሙት ፣ ለእስራኤል ኃፍረት
ነውና።

፪፻፳፫፤ የዘማን የሴሰኝነት ዋጋንና
የውሻን ለውጥ ወደ ቤተ እግዚ
አብሔር አያግቡ፣ ይህ በመጽሐፍ
ያልተዘዘ ነው።

፪፻፳፬፤ ኃብቻ ንጹሕ ነው ፣
የወንድና የሴት አንድ መሆኑንም
እግዚአብሔር አክብሮታል።

፪፻፳፭፤ሰሎሞን አለ የወንድና የወ
ንድ በሩካቤ አንድ አካል መሆን
በእግዚአብሔር ዘንድ የተናቀ
ነው።

፴፩. ዘሌ. ፲፰ — ፳፪
፴፪. ዘዳግ. ፳፯ — ፲፱
፴፫. ዘዳግ. ፳፫ — ፲፯
፴፬. ዕብ. ፲፫ - ፬

፪፻፳፮፤ ወይቤ ዳዊት ብእሲትከ ከመ ወይን ሥሙር ውስተ ጽርሐ ቤትከ ወውሉድከኒ ከመ ተክለ ዘይት ሐዲስ ዐውደ ማዕድከ ናሁ ከመዝ ይትባረክ ብእሲ ዘይፈርሆ ለእግዚአብሔር[፴፭]::

፪፻፳፯፤እስመ ኢመፍትው ለብእሲ መፍቀሬ እግዚአብሔር ይኩን ውስተ ብዙኀ ፍትወት ::

፪፻፳፰፤ ወአንስትኒ ይትአዘዛ ለአምታቲሆን በፍቅር ወበፍርሀት በከመ ብፅዕት ሣራ ትትኤዘዞ ለምታ አብርሃም ወእግዚእየ ትብሎ እስመ ኢሰመየት ስሞ አላ ትቤሎ እግዚእየ ልሂቅ[፴፮] ::

፪፻፳፱፤ወከማሁ አንትሙኒ ዕደው አፍቅሩ አንስቲያክሙ እስመ አባልክሙ እማንቱ ወዕሩያት ምስሌክሙ በልደት[፴፯]::

፪፻፴፤ይቤ አፍቅር ብእሲተከ ዘንዕስከ ከመ ያፈቅር ኀየል ኀበ አንቅዕተ ማያት እስመ እንቲአከ ይእቲ ወትሄሉ ምስሌከ ኵሎ ጊዜ ወአባልከ ይእቲ::

፪፻፴፩፤እስመ ይቤ ዕቀቡ ርእሰክሙ ወኢትድኃሩ አንስቲያክሙ::

፪፻፴፪፤ወበእንተ ትድምርተ ብእሲ ወብእሲት ዘበሕግ ነቂሖሙ እምንዋም ኢይተክዙ ለተሐፅቦ አላ ባሕቱ የሐልዩ ለጸልዮ ወአስተብቍዖ ኀበ እግዚአብሔር::

፴፭ መዝ. ፻፳፯ — ፫
፴፮ ፩. ጴጥ. ፫ — ፮
፴፯ ኤፌ. ፭. ፳፭ — ፳፱

፪፻፳፮፤ዳዊትም ሚስትህ በቤትህ አዳራሽ ውስጥ እንደተወደደ ወይን ናት፣ ልጆችህም በማዕድህ ዙሪያ እንደ አዲስ የዘይት ተክል ናቸው ፣ እነሆ እግዚአብሔርን የሚፈራ ሰው እንዲህ ይባረካል አለ ::

፪፻፳፯፤ እግዚአብሔርን ለሚወድ ሰው በብዙ ፈቃድ ውስጥ ጸንቶ ይኖር ዘንድ አገባብ አይደለምና::

፪፻፳፰፤ሴቶችም ለባሎቻቸው በፍቅርና በፍርሃት ይታዘዙ፣ ክብርት ሣራ ለባሏ ለአብርሃም ትታዘዘው፣ ጌታዬም ትለው እንደነበረ፣ ጌታዬ አለቃዬ ትለው ነበር እንጂ በስሙ አትጠራውም ነበርና::

፪፻፳፱፤እንደዚሁም እናንተ ወንዶች ሆይ ! ሚስቶቻችሁን ውደዱ፣ አካሎቻችሁ ናቸውና፣ በመፈጠርም ከእናንተ ጋር ትክክሎች ናቸውና ::

፪፻፴፤ ዋልያ የውሀ ምንጮችን እንደሚወድ፣ የልጅነት ሚስትህን ውደድ፣የአንተ ናትና፣ ሁለጊዜም ከአንተ ጋር ትኖራለችና፣አካልህም ናትና::

፪፻፴፩፤ራሳችሁን ጠብቁ ሚስቶቻችሁንም አትፍቱ ብሏልና ::

፪፻፴፪፤በሕጋዊ ጋብቻ ስለሚደረግ የወንድና የሴት ግንኙነት ከመኝታቸው በተነሱ ጊዜ ስለ መታጠብ አይጨነቁ ፣ ለጸሎትና ወደ እግዚአብሔር ለመማለድ ያስቡ እንጂ::



፪፻፴፫፤ወእመሰ ዘሰከበ ብእሲተ ካልዕ ወረኵሰ ምስለ ዘማ ወተንሢኦ እመ ተሐፅበ ውስተ ባሕር ወበኵሉ ማያተ አፍላግ ኢይክል ነጺሐ::

፪፻፴፬፤አላ ዳዕሙ ይከውን ክፍሉ ውስተ ኵነኔ ዘለዓለም::

፪፻፴፭፤ ወኢትትዐቀቡ እንከ ሕገ ዘሥጋ እስመ ዘሰብሳብ እሱር ኢኮነ ርኩሰ ወኢትኀሥሡ ፍኖቶሙ ለአይሁድ ወኢትትሐፀቡ ኵሎ ጊዜ ወኢትግበሩ ዘከመ ያለምዱ ተጥህሮ ፤

## አንቀጽ፴ወ፬

በእንተ ከመ መፍትው ይጸልዩ ወይስአሉ ወይዘምሩ ላዕለ እለ አዕረፉ ወየሀቡ ምጽዋተ በእንቲኣሆሙ::

፩፤ ተጋብኡ እንከ ዘእንበለ ሀኬት ውስተ ቤተ ክርስቲያን ወአንብቡ መጻሕፍተ ቅዱሳተ ላዕለ እለ ኖሙ ክርስቲያን ወጻድቃን ወሰማዕት አኃዊክሙ እለ አዕረፉ በሃይማኖተ ክርስቶስ ወግበሩ ሎሙ አኰቴተ ቍርባን ሥጋሁ ቅዱሰ ወደሞ ክቡረ አዕርጉ ውስተ ቤተ ክርስቲያን::

፪፤ወውስተ መቃብርኒ አንብቡ መዝሙረ ቅድሜሆሙ እስመ ይቤ ክቡር ሞቱ ለጻድቅ በቅድመ እግዚአብሔር ግብኢ ነፍስየ ውስተ ዕረፍትኪ እስመ እግዚአብሔር ረዳኢኪ[፩] ::

፩ መዝ. ፻፲፭ ፯ ፤ ፻፲፰ - ፲፰

፪፻፴፫፤ ከሌላውም ሚስት ጋራ የተኛ ከዘማ ጋራ የረከሰ ግን ተነሥቶ በባሕርና በፈሳሾች ውሀ ሁሉ ቢታጠብ መንጻትን አይችልም::

፪፻፴፬፤ክፍሉ በዘለዓለም ፍርድ ውስጥ ይሆናል እንጂ::

፪፻፴፭፤እንግዲህ የሥጋ ሕግን አትጠባበቁ የመጋባት አንድነት ርኩስ አይደለምና ፣ የአይሁድንም መንገድ አትሹ ፣ ሁለጊዜም አትታጠቡ ፣ መጠመቅንም እንደሚያስለምዱ አታድርጉ፤

## ሠላሳ አራተኛ አንቀጽ

በሞቱት ሰዎች ላይ ይጸልዩ፤ ይለምኑና ይዘምሩ ፣ ስለ እነርሱም ምጽዋትን ይሰጡ ዘንድ እንደሚገባ ይናገራል::

፩፤እንግዲህ በቤተ ክርስቲያን ያለ ስንፍና ተሰብሰቡ ፣ በክርስቶስ አምነው ስለ ሞቱ ክርስቲያንና በክርስቶስ አምነው ስለ አረፉ፣ ጻድቃንና ሰማዕታት ወንድሞቻችሁ ቅዱሳት መጻሕፍትን አንብቡ ፣ ቅዱስ ሥጋውንና ክቡር ደሙንም በምስጋና በቤተ ክርስቲያን አሳርጉላቸው::

፪፤ በመቃብርም የዳዊትን መዝሙር በፊታቸው አንብቡ ፣ የጻድቅ ሞት በእግዚአብሔር ፊት የከበረ ነው ፣ እግዚአብሔር ረዳትሽ ነውና ነፍሴ ሆይ ! ወደ ዕረፍትሽ ተመለሽ ይላልና::

፫፤ወካዕበ ይቤ ዝክረ ጻድቅ ለዓለም ይሄሉ በውዳሴ ወነፍሳቲሆሙ ውስተ እደ እግዚአብሔር ፤ እስመ እለ አምኑ በእግዚአብሔር እመኒ ኖሙ ኢኮኑ ምውታነ፡፡

፬፤ ወይቤሎሙ መድኀኒነ ለሰዱቃውያን በእንተ ትንሣኤ ምውታን ኢያንበብክሙኑ ዘይቤ መጽሐፍ አነ ውእቱ እግዚአብሔር አምላከ አብርሃም ወአምላከ ይስሐቅ ወአምላከ ያዕቆብ ኢኮነኬ አምላከ ምውታን አላ አምላከ ሕያውያን ውእቱ[፬]፡፡

፭፤ወአኮ ኵሎሙ ሕያዋን ወኢይትማሰሉ፡፡

፮፤ወኤልሳዕኒ በሞቱ አንሥኦ ለዘቀተልዎ በሶርያ ሶበ ለከፎ በድነ ዚኣሁ ለውእቱ በድን ተንሥአ ፡፡

፯፤ ዮሴፍሂ ጻድቅ ገሠሠ ሥጋሁ ለያዕቆብ በዲበ ዐራት ወኢረኰሰ፡፡

፰፤ሙሴ ወኢያሱ ወልደ ነዌ ሶበ አውጽኡ አዕፅምቲሁ ለዮሴፍ እምብሔረ ግብፅ ለከፉ አዕፅምቲሁ ወኢረኰሱ[፫] ፡፡

፱፤ወከማሁ አንትሙኒ ኤጲስ ቆጶሳት ወኵሉ ሕዝብ ሶበ ገሠሥክሙ በድነ እለ ኖሙ ኢታስቈርሩ ፀዊረ አዕፅምቲሆሙ እስመ ኢኮንክሙ ዘትረኵሱ በእንቲአሆሙ ፡፡

፬ ማቴ. ፳፪. ፴፩ - ፴፪
፫ ዘፀአ. ፲፫ -፲፱

፫፤ ሁለተኛም የጻድቅ መታሰቢያ ለዘለዓለም በምስጋና ይኖራል ፤ ነፍሳቸውም በእግዚአብሔር እጅ ናት ብሏልና፤ በእግዚአብሔር ያመኑ በሞት ቢያንቀላፉም በነፍስ ሙታን አይደሉምና፡፡

፬፤መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ሰዱቃውያንን ስለ ሙታን መነሣት መጽሐፍ እኔ የአብርሃም አምላክ ፤ የይስሐቅም አምላክ ፤ የያዕቆብም አምላክ ነኝ፤ እንኪያስ የሙታን አምላክ አይደለም ፤ የሕያዋን አምላክ ነው እንዲያለውን አላነበባችሁምን አላቸው፡፡

፭፤ግን ሁሉም ሕያዋን አይደሉም ፤ አይመሳሰሉምም፡፡

፮፤ኤልሳዕም በሶርያ የገደሉትን በሞቱ አነሳው ፤ የርሱ በድን (አስከሬን) በነካው ጊዜ የምውቱ በድን ተነሣ ፡፡

፯፤ ጻድቅ ዮሴፍም የያዕቆብን ሥጋ በአልጋው ላይ ዳሰሰ አልረከሰምም ፡፡

፰፤ሙሴና የነዌ ልጅ ኢያሱም የዮሴፍን አፅሞች ከግብጽ አገር ባወጡ ጊዜ አጥንቶቹን ነኩ ፤ ነገር ግን አልረከሱም ፡፡

፱፤እንዲሁም እናንተ ኤጲስ ቆጶሳትና ሕዝብ ሁሉ የሞቱትን ሰዎች በድን በዳሰሳችሁ ጊዜ አጽማቸውን መሸከምን አትጸየፉ፤ስለ እነርሱ የምትረክሱ አይደላችሁምና፡፡



፲፤አሰስሉ እንከ እምኔክሙ ዘንተ ምግባረ እስመ ነገረ ዕበድ ውእቱ፡፡

፲፩፤ወአንትሙሰ ተሠርገዉ በጥበብ ወአእምሮ ከመ ትርከቡ ሕይወተ ዘለዓለም፤ወክፍለ ምስለ ነፍሳተ ጻድቃን በመንግሥተ ሰማያት ውስተ መካነ ዕረፍት በኢየሱስ ክርስቶስ መድኃኒነ ዘይክል ከሢተ እዝነ አልባቢክሙ፡፡

፲፪፤ ከመ ትስምዑ ቃለ እግዚአብሔር ዘመሀሩክሙ በወንጌል፡፡

፲፫፤ወተግሣጸ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ዘተሰቅለ በመዋዕለ ጲላጦስ ጳንጤናዊ ወሄሮድስ ንጉሥ፤ ሐመ ወሞተ ወተንሥአ እሙታን፡፡

፲፬፤ወካዕበ ይመጽእ በስብሐት ወበዐቢይ ኃይል ያነሥኦሙ ለምውታን ወይፈድዮ ለኵሉ በከመ ምግባሩ ወዐርገ በዐቢይ ሰብሐት ኀበ አቡሁ፤

፲፭፤ወእምድኅረ ተንሥአ እሙታን ንሕነ ርኢናሁ በላእነ ወሰተይነ ምስሌሁ ወነበርነ ፵ ዕለተ ምስሌሁ፡፡

፲፮. ወእምድኅረ ፵ ዕለት ዐርገ ሰማያተ ወነበረ በየማነ አብ አኃዜ ኵሉ ዘይነብር ዲበ ኪሩቤል[፭]፡፡

፭ የሐ. ሥራ ፩ — ፱

፲፤ ይህን ሥራ ከናንተ አርቁ ፤ የስንፍና ነገር ነውና፡፡

፲፩፤ እናንተስ የልቡናዎቻችሁን ጆሮ መክፈት በሚችለው በመድኃኒታችን በኢየሱስ ክርስቶስ በዕረፍት ቦታ በመንግሥተ ሰማያት የዘለዓለም ሕይወትንና ከጻድቃን ነፍሳት ጋር ዕድልን ታገኙ ዘንድ በጥበብና በዕውቀት አጊጡ ፡፡

፲፪፤ በወንጌልና በጌታችን ተግሣጽ ያስተማሯችሁን የእግዚአብሔርን ቃል ትሰሙ ዘንድ ፡፡

፲፫፤በጳንጤናዊው በጲላጦስና በንጉሥ ሄሮድስ ዘመን የተሰቀለ ፤ የታመመ፤ የሞተና ከሙታን ተለይቶ የተነሣው የጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስን ተግሣጽ፡፡

፲፬፤ ሁለተኛም በክብርና በታላቅ ኃይል ይመጣል ፤ ሙታንንም ያስነሣቸዋል፤ ለሁሉም እንደየሥራው ይከፍለዋል ፤ በታላቅ ጌትነትም ወደ አባቱ ዓረገ፡፡

፲፭፤ከሙታን ተለይቶ ከተነሣም በኋላ እኛ አየነው ፤ ከእርሱም ጋራ በላን ጠጣን ፵ ቀንም ከእርሱ ጋሪ አብረን ነበርን፡፡

፲፮፤ከ፵ቀን በኋላም ወደ ሰማያት ዓረገ በኪሩቤል ላይ በሚቀመጥ ሁሉን በያዘ በአብ ቀኝም ተቀመጠ ፡፡

፲፯፤ ዘበእንቲአሁ ይቤ ዳዊት ይቤሎ እግዚእ ለእግዚእየ ንበር በየማንየ እስከ አገብኦሙ ለጸላዕትከ ታሕተ መከየደ እገሪከ[፰]::

፲፰፤ወዘርእዮ ብፁዕ እስጢፋኖስ ጸርሐ ወይቤ ናሁ ተርኅወ ሰማይ ወወልደ ዕጓለ እመሕያው ይነብር በየማነ እግዚአብሔር ፈጣሬ ሠራዊተ መላእክት[፱] ዘሎቱ ስብሐት ወአኰቴት ወመንግሥት ምስለ አቡሁ ወመንፈስ ቅዱስ ይእዜኒ ወዘልፈኒ ለዓለመ ዓለም አሜን፤

አንቀጽ፴ወ፫
በእንተ ፃማ ወአኰቴት፤

፩፤ ይቤሎሙ ሙሴ ነቢይ ገሀደ ለደቂቀ እስራኤል ወናሁ አርአይኩክሙ ገሀደ ፍኖተ ሞት ወሕይወት ኅረዩ ለክሙ ሕይወተ ትኅየዉ[፲]::

፪፤ወኤልያስኒ ነቢይ ይቤሎሙ ለሕዝብ እስከ ማዕዜኑ የሐንክስ ልብክሙ ላዕለ እግዚአብሔር አሐዱ ውእቱ እግዚአብሔር ወኪያሁ ኅሡ[፲፩]::

፰ መዝ. ፻፱ — ፩
፱ ሐ. ሥራ ፯ - ፶፭ - ፶፯
፲ ዘዳግ. ፴ . ፲፭ — ፲፱
፲፩ ፩ ነገ. ፲፰ — ፳፩

፲፯፤ ዳዊትም ስለ እርሱ ጌታ ጌታዬን ጠላቶችህን ከእግርህ መረገጫ በታች እስከ አገባቸው በቀኜ ተቀመጥ አለው ያለው ነው::

፲፰፤ ያየው ብፁዕ እስጢፋኖስም አሰምቶ ተናገረ፣ እንዲህም አለ ፣ እነሆ ሰማይ ተከፈተ፣ የሰው ልጅ ክርስቶስ የመላእክት ሠራዊትን በፈጠረ እግዚአብሔር ቀኝ ተቀመጠ ፣ ከአባቱ ከመንፈስ ቅዱስም ጋር ክብር ምስጋናና መንግሥት የእርሱ የሆነ ዛሬም ዘወትርም ለዘለዓለሙ አሜን ::

ሠላሳ አምስተኛው አንቀጽ
የምስጋናንና የድካምን ነገር
ይናገራል ፤

፩፤ ነቢዩ ሙሴ ለእስራኤል ልጆች በግልጥ እንዲህ አላቸው ፣ እነሆ የሞትንና የሕይወትን ጐዳና ገልጬ አሳየኋችሁ ፣ በሕይወት ትኖሩ ዘንድ ለናንተ ሕይወትን ምረጡ ::

፪.ነቢይ ኤልያስም ሕዝቡን እንዲህ አላቸው፣ ልቦናችሁ በእግዚአብሔር ላይ እስከ መቼ ይጠራጠራል? እግዚአብሔር አንድ ነው እርሱን ፈልጉ::



፫፤ ወይቤ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ኢይክል ገብር ለ፪ኤ አጋዕዝት ተቀንዮ ፣ እመ አኮ ለ፩ ይትኤዘዝ ወለካልዑ የአቢ ኢትክሉኬ ተቀንዮ ለእግዚአብሔር ወለንዋይ[፲፪]::

፬፤ወንሕነሰ ተለውናሁ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወመሐርነ ኵሎ ዓለመ ፣ ንብል እንከ ፪ኤ ፍናው እማንቱ አሐቲ እንተ ሞት ወአሐቲ እንተ ሕይወት ፍሉጣን ወአልቦሙ ኅብረት ፩ምስለ ካልዑ ፣ አሐቲ እንተ ትወስድ ውስተ ሞት ወአሐቲ እንተ ትወስድ ውስተ ሕይወት::

፭፤ቀዳሚትሰ ፍና ሕይወት ዘበእንቲአሃ ነገረ ኦሪት ወይቤ አፍቅሮ ለእግዚአብሔር አምላክከ በኵሉ ልብከ ወበኵሉ ኃይልከ ወበኵሉ ነፍስከ አልቦ ባዕድ አምላክ ዘእንበሌሁ ወአፍቅር ቢፀከ ከመ ነፍስከ[፲፫] ::

፮፤ወካልዕታ ዘይቤ ወንጌል ወዘኢትፈቅድ ለርእስከ ኢትግበር ዲበ ካልዕከ ደኅርዎሙ ለእለ ይረግሙክሙ ወጸልዩ ለእለ ይትዔገሉክሙ ወአፍቅሩ ጸላእተክሙ ምንትኑ እንከ ዕሤትክሙ ለእመ አሠነይክሙ ለእለ ያሤንዩ ለክሙ ::

፲፪ ማቴ. ፯ — ፳፬
፲፫ ማቴ. ፳፪ : ፴፯ — ፴፱

፫፤ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም እንዲህ አለ ፣አንድ ባሪያ ለሁለት ጌቶች መገዛትን አይችልም ፣ ወይም ለአንዱ ይታዘዛል ፣ ለአንዱም አይሆንም ይላል እንጂ ፤ እንኪያስ እናንተም ለገንዘብና ለእግዚአብሔር መገዛትን አትችሉም ::

፬፤እኛም አነሆ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስን ተከተልነው ፣ ዓለሙንም ሁሉ ይቅር አልን ፣ እንግዲህ እንዲህ እንላለን ፣ ሁለት መንገዶች አሉ፣ አንዲቱ የሞት አንዲቱ የሕይወት ፣ አንዱ ከአንዱ ጋራ መተባበር የሌላቸው የተለያዩ ናቸው ፣ አንዲቱ ወደ ሞት ትወስዳለች ፣ አንዲቱም ወደ ሕይወት ትወስዳለች::

፭፤መጀመሪያይቱ ኦሪት ስለ እርሷ የተናገረላት የሕይወት ጐዳና ናት ፣ እንዲህም አለ፣ አምላክህ እግዚአብሔርን በፍጹም ልብህ፣ በፍጹም ኃይልህ፣በፍጹም ነፍስህ ውደደው፣ ከእርሱ በቀርም ያለ እርሱ ሌላ አምላክ የለምና ፣ ባልንጀራህንም እንደ ራስህ ውደድ::

፮፤ሁለተኛዪቱም ለራስህ የማትወደውን በባልንጀራህ ላይ አታድርግ፣ የሚረግሟችሁን መርቋቸው ፣ ለሚቀሟችሁም ጸልዩላቸው፣ ጠላቶቻችሁን ውደዱ፣ በጎ ላደረጉላችሁማ በጎን ብታደርጉ ዋጋችሁ ምንድር ነው ? ብሎ ወንጌል የተናገራት ናት ::

፯፤ወአንትሙሰ ዑቁ ኢትጽልኡ ወኢመነሂ::

፰፤ ወካዕበ ይቤ ኢትጽላእ ኵሎ ሰብአ ኢግብፃዌ ወኢ ኤዶማዌ እስመ ኵሉ ፍጥረተ እግዚአብ ሔር እሙንቱ::

፱፤ ወረንቀሰ እምእኩያን ሰብእ ወእምፍትወተዝ ዓለም::

፲፤ወለዘሂ ጸፍአከ መልታሕቴከ ዘየማን ሚጥ ሎቱ ካልዕታ::

፲፩፤ እስመ ይቤ ዳዊት እመኒ ፈደይክዎሙ ለእለ ይፈድዩኒ እኩየ ለያውድቁኒ ጸላእትየ ዕራ ቅየ[፭]::

፲፪፤ወካዕበ ይቤ ወለዘሂ አበጠከ ፩ ምዕራፈ ሑር ምስሌሁ ፪ ወለዘሂ ነሥአ ልብሰከ ኅድግ ሎቱ ክዳነከ ወለዘሂ ሐደ ንዋየከ ኢትክልአ ወለዘሂ ሰአለከ ሀቦ ወለዘይፈቅድ ይትለቃሕ እምኔከ ኢትዕጹ ኆኅ ተከ[፮]::

፯፤እናንተ ግን ማንንም እንዳት ጠሉ ዕወቁ::

፰፤ሁለተኛም ሰውን ሁሉ አት ጥላ ፤ ግብፃዊውንም ቢሆን ፤ ኤዶማዊውንም ቢሆን ሁሉም የእግዚአብሔር ፍጥረቶች ናቸ ውና ::

፱፤ነገር ግን ከክፉ ሰዎችና ከዚህ ዓለም ፈቃድ ራቁ::

፲፤ቀኝ ጉንጭህን ለመታህ ሰው ሁለተኛይቱን መልስለት ::

፲፩፤ዳዊት ክፉ ለአደረጉብኝ ክፉን ብመልስላቸው ጠላቶቼ ዕራቁቴን ይጥሉኝ ብሏልና::

፲፪፤ሁለተኛም አለ ፤ ማንም ሰው አንድ ምዕራፍ እንድትሄድ ቢያስገ ድድህ ሁለተኛውንም ምዕራፍ ከእ ርሱ ጋር ሂድ ፤ እጀ ጠባብህ ንም ሊወስድ ለሚወድ መጐናጸፍ የህን ደግሞ ተውለት ፤ገንዘብህን ለሚቀማህ አትከልክለው ፤ ለሚለ ምንህም ስጠው ፤ ከአንተ ሊበደር የሚወደውንም በርህን አትዝጋ በት ::

፭ መዝ. ፯ — ፭

፮ ማቴ. ፭ - ፵፩



፲፫፤እስመ መፍቀሬ ሰብእ መሐሪ ይሁብ ለኵሉ ለዘሰአሎ ወእግዚ አብሔር አብ ያሠርቅ ፀሐየ ላዕለ እኩያን ወኄራን ወያዘንም ዝናመ ላዕለ ጻድቃን ወኃጥኣን[፯]::

፲፬፤መፍትው ተሀቡ ለኵሉ እምፃማ እደዊክሙ ወታክብርዎሙ ለቅዱ ሳን እስመ ይቤ ኢትቅትል ነፍሰ አርአያከ ወአምሳሊከ ወአልቦ ዘየ አኪ እምቀቲል::

፲፭፤ ወኢትዘሙ ወኢትፍልስ እምነ ሥጋከ ወኢትረሲ ፪ኤ ክፍለ እስመ ይቤ ይከውኑ ፪ሆሙ ፩ ሥጋ[፰] ወ፩ መንፈስ ወበአርአያሰ ፍሉጣን እሙንቱ::

፲፮፤ወኢትስርቅ እስመ ሶበ ሰረቀ አካን እስራኤላዊ ወገርኖ በአዕባን ወወጽአ እምሕይወት[፱]::

፲፯፤ወከማሁ ግያዝኒ ሰረቀ ወሀ ሰወ ወለብሰ ለምጸ ለንዕማን ሶር ያዊ[፲]::

፲፰፤ወይሁዳኒ አስቆሮታዊ ሰረቀ ሙዳየ ምጽዋት ዘይሁቡ ምጽዋተ ለነዳያን ወአግብኦ ለእግዚአ ስብሐት ውስተ እደዊሆሙ ለአይሁድ[፲፩]::

፲፱፤ወእምዝ ነሥሐ ወተሐንቀ ወተክዕወ አማዑቱ ወሞተ[፲፪]::

፲፫፤ሰውን ወዳጅ እርሱ ቸር ነውና ለለመነው ሁሉ ይሰጣል፣ እግዚአብሔር አብም በክፉዎችና በደጋጎች ላይ ፀሐይን ያወጣል፣ በጻድቃንና በኃጥአን ላይም ዝና ምን ያዘንማል::

፲፬፤ ከእጆቻችሁ ድካም ለሁሉ ትሰጡ ዘንድ ቅዱሳንንም ታከብሩ ዘንድ ይገባል፣ የመልክህንና የምሳ ሌህን ነፍስ አትግደል ይላልና፣ ነፍስን ከመግደል የሚከፋ የለምና::

፲፭፤ አትሰስን፣ ከአካልህም ተለይ ተህ ሁለት ክፍልን አትሁን፣ ሁለቱ አንድ አካል፣ አንድ ልቡና ይሆናሉ፣ በአስታያየት ግን ልዩ ዎች ናቸው ብሏልና::

፲፮፤ አትስረቅ፤እስራኤላዊው አካን በሰረቀ ጊዜ በድንጊያ ደብድበነው ከሕይወትም ወጥቷልና ::

፲፯፤እንዲሁም ግያዝ ሰርቆ በዋሸ ጊዜ የሶርያዊ የንዕማንን ለምጽ ለበሰ::

፲፰፤የአስቆሮቱ ሰው ይሁዳም ለድ ሆች የሚሰጡትን ምጽዋት ሰረቀ፣ የክብር ጌታንም በአይሁድ እጆች አሳልፎ ሰጠው::

፲፱፤ከዚህም በኋላ ተጸጽቶ ታነቀ፣ አንጀቱም ተዘርግፎ ሞተ::

፯ ዮሐ.፲፪.፯
፰ ማቴ ፭: ፵፭
፱ ማቴ ፲፱: ፭
፲ ኢያሱ ፯: ፲፯ - ፳፬
፲፩ ፪ ነገሥ ፭: ፳- ፳፯
፲፪ የሐ.ሥራ.፭.፲፰-፲፱

፳፡ ሐናንያ ወሰጲራ ብእሲቱ ቀሰጡ መንፈቀ ሤጠ ንዋዮሙ ወሐሰውዎ ለመንፈስ ቅዱስ ወሞቱ በኀበ ፍቁር እኁነ ጴጥሮስ ሐዋርያ[፲፫]::

፳፩፡ ኢታስግሉ ወኢታጣዕዉ ወኢትሕትቱ ማርያ እስመ ይቤኢትትአመንዎሙ ለማርያን::

፳፪፡ ወኢትቅትል ውሉደ በሙስና እስመ አርአያሁ ወመንፈሱ፤ ለእግዚአብሔር ውእቱ ::

፳፫፡ ወኢታፍቅር ንዋዮ ለእኁከ ወኢብእሲቶ ወኢገብሮ ወኢአመቶ ወኢአድጎ ወኢላህሞ[፲፬]::

፳፬፡ ወዓዲ ይቤ ኢትምሐል ግሙራ በሐሰት ወእመሰ መሐልከ መሐል በጽድቅ[፲፭]::

፳፭፡ ወካዕበ ይቤ ኢትኩን ስምዐ በሐሰት እስመ ዘይነብብ ሐሰተ ላዕለ ነዳያን ያምዕዕ ፈጣሪሁ[፲፮]::

፳፮፡ ወፍኖቶሙ ለገባርያነ እኪት ይወስድ ኀበ ሞት::

፳፯፡ ኢትኩን ዘ፪ ልቡ ወዘ፪ ልሳኑ እስመ መሥገርቱ ለሰብእ ንባበ አፉሁ ወብእሲ ነባቢ ኢያረትዕ ሀዲበ ምድር [፲፯]::

፲፫ የሐ.ሥራ ፭:፩-፲፩
፲፬ ዘፀ. ፳ ÷ ፲፯
፲፭ ማቴ ፭ : ፴፫-፴፯
፲፮ ዘፀ.፳ ፲፮
፲፯ መዝሙ፡ ፻፴፱. ፲፪

፳፡ ሐናንያና ሚስቱ ሰጲራም የገንዘባቸውን ሽያጭ እኩሌታ ሰርቀው መንፈስ ቅዱስን ዋሹት፤ በተወደደ ወንድማችን በጴጥሮስም ዘንድ ሞቱ::

፳፩፡ አታስጠንቍሉ፣ ጣዖትንም አታምልኩ፣ ጠንቋይንም አትመርምሩ፣ ጠንቋዮችን አትመኗቸው፣ ብሏልና::

፳፪፡ ልጆችንም በማስወረድ አትግደል፣ የእግዚአብሔር አርአያውና አምሳሉ ናቸውና ::

፳፫፡ የወንድምህን ገንዘብ ሚስቱን፣ ወንድ ባሪያውን፣ ሴት ባሪያውን አህያውንና ላሙን አትውደድ ::

፳፬፡ ዳግመኛም «በሐሰት ፈጽመህ አትማል፣ ብትምል ግን በእውነት ማል» አለ ::

፳፭፡ ሁለተኛም በሐሰት ምስክር አትሁን፣ በድሆች ላይ ሐሰትን የሚናገር ሰው ፈጣሪውን ያስቆጣልና::

፳፮፡ የክፉ አድራጊዎች መንገድ ወደ ሞት ይወስዳል::

፳፯፡ ልቡ ሁለት፤ አንደበቱም ሁለት የሆነ ሰውን አትሁን፣ የሰው ወጥመዱ የአፉ ነገር ነውና ተናጋሪ ሰውም በምድር አይጸናም::



፳፰፡ ወኢይኩን ቃልክሙ ጽሩዐ እስመ ኵሉ ሰብእ ዘይነብብ በከመ ረከበ ይትኴነን ::

፳፱፡ ወኢትምስጥ እስመ ይቤ አሌ ሎሙ ለእለ ይዔምፁ አዕርክቲሆሙ ::

፴፡ ወኢትኩን ነሣኤ ገጽ ወኢጽልሑወ ልብ ወኢዝኁረ እስመ እግዚአብሔር የኃሥሮሙ ለዕቡያን::

፴፩፡ ወኢትጽላእ ኵሎ ሰብአ ወኢትርግም እኁወከ ወኢትግበር ምስሌሁ ኀሡመ ወተገኀሥ እምኵሉ እኩይ፤

፴፪፡ ወኢትኩን መዐትመ ወኢቀናዔ ከመ ኢይርከብከ ዘረከቦሙ ለቃየል ወለሳኦል ወለኢዮአብ እስመ ቃየል ቀተለ አቤልሃ እኁዋሁ ዘኃረዮ እግዚአብሔር ወተወክፈ መሥዋዕቶ[፲፰]::

፴፫፡ ወሳኦልኒ ሰደዶ ለዳዊት ሶበ ሞዖ ለጎልያድ ኢሎፍላዊ ቀንአ ላዕሌሁ በእንተ ማኅሌት ዘሐለያ አንስት[፲፱]::

፴፬፡ ወኢዮአብኒ ቀተሎ ለአቤኔር እስራኤላዊ ወለአሜሳይ ዘይሁዳ[፳]::

፲፰ ዘፍ ፬: ፰
፲፱ ፩.ሳሙ ፲፰:፯-፳፱
፳ ፪ሳሙ. ፫:፯-፴፤፳:፱-፲

፳፰፡ ቃላችሁ ተርታን አይሁን እንዳገኘ የሚናገር ሰው ሁሉ ይፈረድበታልና ::

፳፱፡ አትንጠቅ፣ ወዳጆቻቸውን ለሚበድሉ ሰዎች ወዮላቸው ብሏልና::

፴፡ ፊት አይተህ የምታደላ በልብ የምትሸነግልና ትዝኅርተኛ አትሁን፤ እግዚአብሔር ትዕቢተኞችን ያዋርዳልና ::

፴፩፡ ሰውን ሁሉ አትጥላ ወንድምህንም አትርገም ከእርሱ ጋራም ክፉን አትሥራ ከክፉም ሁሉ ተለይ::

፴፪፡ ቁጡና ቀናተኛም አትሁን ቃየልን፣ ሳኦልን ፣ ኢዮአብንም ያገኛቸው እንዳያገኝህ ፣ ቃየል እግዚአብሔር የመረጠውን መሥዋዕቱንም የተቀበለለትወንድሙን አቤልን ገድሏልና ::

፴፫፡ ሳኦል የኢሎፍሊ ሰው ጎልያድን ድል በነሳው ጊዜ ሴቶች ስለዘፈኑለት ዘፈን በእሱላይ ቀንቶ ዳዊትን አሳድዶታ ልና::

፴፬፡ ኢዮአብ የእስራኤልን ወገን አቤኔርንና የይሁዳ ሰው አሜሳይን ገደለ ::

፴፭፤ ወኢይኩን መሰግለ በአዕዋፍ እስመ ይመርሖ ውስተ አጣዕዎ።

፴፮፤ ወበእንቲአሁ ይቤ ሳሙኤል ዝግብር ኀጢአት ውእቱ ወኢይከውን ከመዝ በውስተ እስራኤል እስመ ዝ ኵሉ ምኑን ውስተ ሕግ[፩፩]።

፴፯፤ ወኢትኩኑ መንጐርጕራነ እስመ ሰማዕክሙ ዘረከቦሙ ለእለ አንጐርጐሩ ላዕለ ሙሴ ወዳዊት[፩፪] ፤ እስመ የዋሃን ይወርስዋ ለምድር።

፴፰፤ኩኑኬ መሐርያነ እስመ እሙንቱ ይትሜሐሩ።

፴፱፤ ተወከፍ ኵሎ ፃማከ ዘይመጽእ ላዕሌከ ከመ ኢዮብ ወአልዓዛር ከመ ትንሣእ ዕሤተ በኀበ እግዚአብሔር።

፵፤ወአክብር ዘይሜህረከ ቃለ እግዚአብሔር ወተዘከሮ መዓልተ ወሌሊተ፤

፵፩፤እስመ ኀበ ሀሎ ተግሣጽ ህየ ሀሎ እግዚእ ።

፵፪፤ወዕርቆሙ ለእለ ቦሙ ተስናን ወፍታሕ በርትዕ እስመ ፍትሕሰ ለእግዚአብሔር ውእቱ።

፩፩ ፩ሳሙ ፲፭፡፩፫
፩፪ ዘኍ ፲፪፡፩-፲፮

፴፭፤ በዎፎች የሚያሟርት አይሁን፣ ጣዖትን ወደማምለክ ይመራዋልና።

፴፮፤ ስለሱም ሳሙኤል ይህ ሥራ ኃጢአት ነው፣ እንዲህ ያለ ሥራም በእስራኤል ውስጥ አይደረግም፣ ይህ ሁሉ በመጽሐፍ የተናቀ ነውና።

፴፯፤ አንጐርጓሪዎችን (አጕረምራሚዎችን) አትሁኑ፣ በዳዊትና በሙሴ ላይ ያጕረመረሙትን ያገኛቸውን ሰምታችኋልና፣ የዋሃን ኃዳግያን በቀል ምድርን የሚወርሷት ስለሆነ ።

፴፰፤የምታዝኑ የምትራሩ ሁኑ የሚያዝኑ የሚራሩ ሰዎች ይቅር ይባላሉና ።

፴፱፤በአንተ ላይ የሚመጣውን መከራ ሁሉ ተቀበል፣ እንደ ኢዮብና እንደ አልዓዛር ከእግዚአብሔር ዋጋህን ትቀበል ዘንድ ።

፵፤የእግዚአብሔርን ቃል ያስተማረህን አክብር በቀንና በሌሊትም አስበው።

፵፩፤ምክር ከአለበት እግዚአብሔር ከዚያ አለና።

፵፪፤ጠብ ያለባቸውን ሰዎች አስታርቃቸው፣ በዕውነትም ፍረድ፣ ፍርድ ለእግዚአብሔር ነውና ።



፵፫፤ወሶበ ትጼሊ ኢትኩን ዘ፪ኤልቡ ፣ እስመ ይቤ ጴጥሮስ ዘይቤለኒ ሊተ እንዘ ሀሎኩ ውስተ ባሕር ለምንት ትናፍቅ ወትሬሲ ፪ ልበ[፩፫]።

፵፬፤ወአመኒ ወሀብከ ምጽዋተ ለነዳያን ኢትናፍቅ አእምር እንከ መኑ ውእቱ ፈዳዩ ዐስብ አኮኑ እግዚአብሔር ።

፵፭፤ሀብኬ ጻሕቆ ለኵሉ ለዘሰአለከ ወኢትርሳዕ ኵሎ ትእዛዛቲሁ ለእግዚአብሔር ።

፵፮፤ወእመሰ አበስከ ቅድሜሁ ኢትጌጊ ዳግመ ከመ ትርከብ ሠናየ በቅድመ እግዚአብሔር አምላክከ እስመ ኢይፈቅድ ሞቶ ለኃጥእ አላ ይትመየጥ ለንስሓ።

፵፯፤ወአክብር አባከ ወእመከ ኢትትሐየይ አኃዊከ ወአዝማዲከ[፩፬]።

፵፰፤ተቀነይ ለንጉሥ ወአእምር ከመ እምኀበ እግዚአብሔር ሢመቱ ወአክብር መኳንንተ እስመ ላእካነ እግዚአብሔር እሙንቱ ።

፵፱፤ወኢታዕርግ መሥዋዕተ እንዘ ትገብር እኩየ ዘእንበለ ትነስሕ እምእከየ ምግባሪከ።

፩፫ ዘዐ. ፩. ፲፪

፵፫፤በምትጸልይበት ጊዜም ሁለት ልብ አትሁን፣ ጴጥሮስ በባሕር ሳለሁ እኔን ለምን ትጠራጠራለህ ልብህንስ ለምን ሁለት ታደርጋለህ አለኝ ብሏልና።

፵፬፤ለድሆችም ምጽዋትን በሰጠህ ጊዜ አትጠራጠር፣ እንግዲህ ዋጋ የሚከፍል ማን እንደሆነ ዕወቅ፣ እግዚአብሔር አይደለምን?

፵፭፤ለለመነህ ሁሉ ግዳጁን ስጠው፣ የእግዚአብሔርንም ትእዛዞች ሁሉ አትርሣ ።

፵፮፤በእርሱ ፊት ብትበድል ግን ዳግመኛ አትበድል፣ በፈጣሪህ እግዚአብሔር ፊት በጐ ነገርን ታገኝ ዘንድ በንስሓ ይመለስ ዘንድ ነው እንጂ ፣ የኃጢአተኛን ሞት አይወድምና።

፵፯፤ አባትህንና እናትህን አክብር፣ ዘመዶችህንና ወንድሞችህንም ቸል አትበል።

፵፰፤ ለንጉሥም ተገዛ ሹመቱም ከእግዚአብሔር ዘንድ እንደሆነ ዕወቅ፣ ገዢዎችን አክብር፣ እነርሱ የእግዚአብሔር መልእክተኞች ናቸውና ።

፵፱፤ከክፉ ሥራህ ሳትመለስ ክፉ እየሠራህ መሥዋዕትን አታቅርብ።

፶፡ዛቲ ይእቲ ፍኖተ ሞት ወሕይ
ወት ወይረሲክሙ እግዚአብሔር
ድልዋነ ትትልዉ ፍኖቶ ለእግዚ
እነ ኢየሱስ ክርስቶስ፡፡

## አንቀጽ ፴ወ፯
### በእንተ ሜሮን

፩፡ነአኵተከ ከመዝ፣ ነአኵተከ ኦ
ፈጣሬ ኵሉ በእንተ መዓዛ ዝንቱ
ሜሮን ወበእንተ ዝንቱ ዘይት፣
ዘአልቦ ሞት ዘከሠትከ ለነ በኢየ
ሱስ ክርስቶስ ወልድከ፣እስመ ለከ
ስብሐት ወመንግሥት ወኃይል ለዓ
ለመ ዓለም አሜን፡፡

፪፡ወለዘኒ ይመጽእ ኀቤክሙ ወየ
አኵት ከመዝ ተወከፍዎ እስመ
ረድአ ክርስቶስ ውእቱ፡፡

፫፡ ወእመሰቦ ዘይሜህር ካልዐ
ትምህርተ ዘእንበለ ሕግ ዘተውህበ
ለክሙ እምኀበ እግዚአብሔር ኢት
ትወከፍዎ ወኢይኅበር ምስሌክሙ
ውስተ አኰቴት፡፡

፬፡ወለኵሉ ዘይመጽእ ኀቤክሙ
አመክርዎ ወጠይቀክሙ ምግባሮ
ሥርዐ በከመ ይደሉ እስመ ብክሙ
አእምሮ የማን እምጸጋም ወፍ
ትሑ ማዕከለ እለ ይኴንኑ በጽድቅ
ወይኴንኑ በዐመፃ፡፡

፭፡ወለቢጽክሙ ዘይፈትሕ በጽ
ድቅ አሠንዩ ሎቱ በከመ ምግ
ባሩ፡፡

፶፡የሞትና የሕይወት ጎዳና ይህች
ናት፣ እግዚአብሔርም የጌታችን
የኢየሱስ ክርስቶስ ጐዳናን ትከ
ተሉ ዘንድ የተዘጋጃችሁ፤ ያድርጋ
ችሁ፡፡

## ሠላሳ ስድስተኛ አንቀጽ
### የሜሮንን ነገር ይናገራል፤

፩፡ እንደዚህ እናመሰግንሃለን፤
የሁሉ ፈጣሪ ሆይ! በልጅህ በኢየ
ሱስ ክርስቶስ ለኛ ስለገለጥክልን
ሞት ስለሌለበት ስለዚህ ሜሮን
መዓዛ ስለዚህ ዘይት እናመሰግን
ሃለን፣ ክብር መንግሥት ኃይል
ለአንተ ነውና ለዘለዓለሙ አሜን፡፡

፪፡ወደናንተም መጥቶ እንደዚህ
የሚያመሰግነውን ተቀበሉት፣ የክ
ርስቶስ ደቀ መዝሙር ነውና፡፡

፫፡ከእግዚአብሔር ዘንድ ለእናንተ
ከተሰጠ ሕግ በቀር ሌላ ትምህርት
የሚያስተምር ቢኖር ግን አትቀበ
ሉት፣ በምስጋናም ከእናንተ ጋራ
አይተባበር ፡፡

፬፡ ወደ እናንተ የሚመጣውንም
ሁሉ ፈትኑት፣ ሥራውንም ተረድ
ታችሁ እንደሚገባ ወስኑ፣ ቀኙን
ከግራው የመለየት ዕውቀት አላች
ሁና በእውነት በሚፈርዱና በዐ
መፅ በሚፈርዱ መካከል ፍረዱ፡፡

፭፡በእውነት ለሚፈርድ ባልንጀራ
ችሁም እንደ ሥራው በጎ አድር
ጉለት ፡፡



፮፡ወሶበ ይፈትሕ በዐመፃ ፍድይዎ
በከመ ምግባሩ ወኢትጸልዩ ምስ
ሌሁ ከመ ኢትርከሱ ምስሌሁ
ኅቡረ፡፡

፯፡ ወኵሉ ነቢይ መገሥጽ ዘይመ
ጽእ ኀቤክሙ ወይሜህር በጽድቅ
ይደልዎ ሲሳዩ ከመ ገብር ኄር
ዘይትቀነይ ለእግዚአብሔር[፩]፡፡

፰፡ለካህናትኒ ሀብዎሙ ቀዳሜ ፍሬ
ያት ከመ ይባርኩ ተግባረክሙ[፪]
ወኵሎ ዐሥራተ ሀቡ ለእቤራት ወለ
ዕጓለ ማውታ ወለአናግድ ወለግዩ
ራን፡፡

፱፡ወበዕለተ ሰንበት እንተ ይእቲ ትን
ሣኤሁ ለእግዚእነ ተጋብኡ ውስተ
፩ መካን ወአዕኵትዎ ለእግዚአብ
ሔር በእንተ ኵሉ ዘገብረ ለክሙ
ሠናያተ በክርስቶስ ከሙ ይኩን መሥ
ዋዕትክሙ ፍጹመ ወሥሙረ በኀበ
እግዚአብሔር ፡፡

፲፡እስመ ይቤ በእንተ ቤተ ክርስ
ቲያን ከመ ይትጋብኡ ውስቴታ
ወያዕርጉ ዕጣነ ወመሥዋዕተ ፡፡

፲፩፡ወይቤ እግዚአብሔር አነ ውእቱ
እግዚአብሔር ዐቢይ ንጉሥ አኃዜ
ኵሉ ዓለም ወግሩም ስምየ ውስተ
ኵሉ ዓለም ወአሕዛብ[፫]፡፡

፮፡በበደል በሚፈርድ ጊዜም እንደ
ሥራው ፍዳ ክፈሉት፤ ከእርሱም
ጋራ በአንድነት እንዳትረክሱ ከእ
ርሱ ጋራ አትጸልዩ፡፡

፯፡ወደ እናንተ የሚመጣና በእው
ነት የሚያስተምር መካሩ ነቢይ (መም
ህር) ሁሉ ለእግዚአብሔር እንደሚያገለ
ግል ደግ አገልጋይ ምግቡ ይገባዋል ፡፡

፰፡ለካህናትም ሥራችሁን ይባርኩ
ዘንድ ከፍሬዎች መጀመሪያ የሚ
ደርሰውን ስጧቸው፣ አሥራት
ንም ሁሉ ለባልቴቶችና ለድሃ አደ
ጎች እናት አባት ለሞቱበት ለእንግ
ዶችና ለድሆች ስጡ፡፡

፱፡የጌታችን ትንሣኤ በምትሆን በሰንበት
ቀን በአንድ ቦታ ተሰብሰቡ፣ መሥዋ
ዕታችሁ በእግዚአብሔር ዘንድ ፍጹ
ምና የተወደደ እንዲሆን በኢየሱስ
ክርስቶስ ለናንተ በጎዎችን ስለአደረገ
ላችሁ ሁሉ እግዚአብሔርን አመስግ
ኑት፡፡

፲፡ ስለ ቤተ ክርስቲያን በውስጧ
ተሰብስበው መሥዋዕትንና ቍርባ
ንን ያሣርጉ ብሏልና ፡፡

፲፩፡ እግዚአብሔርም እንዲህ አለ፣
እኔ ዓለሙን ሁሉ የያዘ ገናና ንጉሥ
እግዚአብሔር ነኝ፣ ስሜም በአሕ
ዛብና በዓለሙ ውስጥ የሚያስፈራ
ነው አለ ፡፡

፩ ማቴ ፲ ፡ ፲
፪ ዘኊ ፲፰. ፲፪
፫ ሚል ፩. ፲፩

፲፪፡ሚሙ ለክሙ ኤጲስ ቆጶሳተ ቀሳውስተ ወዲያቆናተ የዋሃነ ወትሑታነ እለ ተኅርዩ እምሕዝብ ንጹሓን ወምኩራነ በኵሉ ምግባረ ሠናይ እለ ኢይፈቅዱ ወርቀ አላዳዕሙ እለ ይሜህሩ ቃለ እግዚአብሔር ወተግሣጸ ወይፈትሑ በርትዕ ትእዛዛቲሁ ለክርስቶስ ከመ አብ ወእግዚእ በፍቅር ዘእንበለ መዓት ወቍጥዓ በትሑት ልብ ወየዋሃት።

፲፫፡ወዕቀቡ ዘንተ ኵሎ ዘተአዘዝክሙ በኀበ እግዚአብሔር ለሕይወተ ነፍስክሙ ።

፲፬፡ቅንቱ ሐቌክሙ ወይኩን ኀትወ መሐትዊክሙ ወኩኑ ድልዋነ ከመ እለ ይጸንሑ እግዚኦሙ እንዘ ይብሉ ማእዜ ይመጽእ እመኒ በቀዳሚት ሰዓተ ሌሊት፣ ወእመኒ መንፈቀ ሌሊት፣ አው በንቅወተ ዶርሆ፣ ወእመኒ ጎሐ ጽባሕ እስመ ይመጽእ እግዚኦሙ በጊዜ ኢተሐዘቡ።

፲፭፡ብፁዓን እሙንቱ አግብርት ዘአቲዎ እግዚኦሙ ይረክቦሙ እንዘ ከመዝ ይገብሩ ናሁ ይቀንት ወያንሶሱ ወይሜጥዎሙ[፩] ።

፲፮፡ጸልዩ እንከ ወግበሩ ከመ ኢይርከብክሙ ግብተ ሞት ወአመ ያስተርኢ በሰማይ ስብሐቲሁ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው

፲፪፡የዋሃንና ትሑታን የሆኑ ፣ከንጹሓን ሕዝብ የተመረጡ በበጎ ሥራ ሁሉ የተፈተኑ፣ ወርቅን የማይወዱ፤ነገር ግን የእግዚአብሔርን ቃልና ምክር የሚያስተምሩ፣ የክርስቶስንም ትእዛዞች እንደ አባትና ጌታ በፍቅር ያለ ብስጭትና ያለ ቁጣ በትሑት ልብና፣ በየዋህነት ፣ በቅንነት የሚፈርዱ ኤጲስ ቆጶሳትን፣ ቀሳውስትንና ዲያቆናትን ሹሙ ።

፲፫፡ስለ ነፍሳችሁ ሕይወትም በእግዚአብሔር ዘንድ የታዘዛችሁትን ይህን ሁሉ ጠብቁ ።

፲፬፡ወገባችሁን ታጠቁ መብራታችሁም የበራ ይሁን፣ በመጀመሪያ ሰዓተ ሌሊት፣ ወይም በመንፈቀ ሌሊት፣ ወይም ዶሮ ሲጮህ፣ ወይም ጎህ ሲቀድ ይመጣል ብለው ጌታቸውን እንደሚጠብቁ የተዘጋጃችሁ ሁኑ፤ ጌታቸው ባልተጠረጠረ ሰዓት ይመጣልና።

፲፭፡ጌታቸው በተመለሰ ጊዜ እንደዚህ ሲያደርጉ የሚያገኛቸው አገልጋዮች ብፁዓን ናቸው፣ እነሆ ታጥቆ እየተመላለሰ በማዕድ ያገለግላቸዋል።

፲፮፡እንግዲህ ጸልዩ፣ የድንገት ሞት እንዳያገኛችሁም አድርጉ፤ የወልደ ዕጓለ እመሕያው ጌትነትም በሚገለጥበት ጊዜ መላእክትም መለከት

[፩] ሉቃ ፲፪ ፴፯



ወይነፍሑ ቀርነ መላእክት ወይትነሥኡ ሙታን ወይመጽእ እግዚእነ ምስለ ቅዱሳኒሁ በደመና ሰማይ ወኵሎሙ መላእክተ ኃይሉ ምስሌሁ ወይነብር ዲበ መንበረ መንግሥቱ ወያሀጕሎ ለዲያብሎስ መስሕት ወይፈድዮ ለኵሉ በከመ ምግባሩ።

፲፯፡ወእምዝ የሐውሩ ኃጥአን ውስተ ኵነኔ ዘለዓለም፣ ወጻድቃንሰ ውስተ ሕይወት ዘለዓለም[፫]። ወይትፌሥሑ በመንግሥተ ሰማያት በእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ኩኑኬ ድልዋነ ከመ ትርከቡ ሠናይቶ።

፲፰፡ ንስአል ወናስተብቍዕ ኀቤሁ ወንበል መድኃኒነ ዘህልው እምቅድመ ዓለም አምላከ አማልክት አኃዜ ኵሉ ፩ አምላክ ገባሬ ኵሉ ፍጥረት እግዚኦሙ ለአበዊነ ቅዱሳን ዘአልቦሙ ዐመፃ በኀቤሁ አምላከ አብርሃም ይስሐቅ ወያዕቆብ መሓሪ ወሰራዬ ኀጢአት ምእመን ወየዋህ ብዙኀ ሣህል ወምሕረት ወአልቦ ዘይትኀባእ እምኔሁ ወኵሉ ክሡት በቅድሜሁ።

፲፱፡ ብከ ይትአመኑ ነፍሳተ ጻድቃን ወኪያከ ይሴፈዉ ቅዱሳን

በሚነፋበት ጊዜ ፣ ሙታንም በሚነሡበት ጊዜ ጌታችንም ከቅዱሳኑ ጋር በደመና በሚመጣ ጊዜ፣ የሠራዊቱ አለቆች ሁሉም ከእርሱ ጋር በመጡ ጊዜ፣ በመንግሥቱ ዙፋንም በሚቀመጥ ጊዜ ፣ የሚያስት ዲያብሎስንም በሚያጠፋው ጊዜ፣ ለሁሉም እንደ ሥራው በሚከፍለው ጊዜ ።

፲፯፡ከዚህ በኋላ ኃጥአን ወደ ዘለዓለም ፍርድ በሚሄዱ ጊዜ፣ ጻድቃን ግን ወደ ዘለዓለም ሕይወት በሚሄዱ ጊዜ፣ በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስም በመንግሥተ ሰማያት ደስ በሚላቸው ጊዜ ፣ የድንገት ሞት እንዳትሞቱ አድርጉ፣ እንግዲህ በጎውን ታገኙ ዘንድ የተዘጋጃችሁ ሁኑ።

፲፰፡ወደ እርሱ እንለምን፤እንማልድም፤ ከዓለም አስቀድሞ የነበረ መድኃኒታችን የአማልክት አምላክ ሁሉን የያዘ፣ ፍጥረትን ሁሉ የፈጠረ አንድ አምላክ በእርሱ ዘንድ ዐመፅ የሌለባቸው የቅዱሳን አባቶቻችን ጌታ የአብርሃምና የይስሐቅ፤ የያቆብም አምላክ ይቅር ባይና ኃጢአትን የሚያስተሠርይ የታመነ የዋህ ይቅርታንና ቸርነትን የሚያበዛ ከእርሱ የሚሸሸግ የሌለ ሁሉም በእርሱ ፊት የተገለጠ ነው እንበል።

፲፱፡የጻድቃን ነፍሳት በአንተ ይታመናሉ፣ቅዱሳን አንተን ያመሰግናሉ ፣

[፫] ማቴ ፳፭ ፡ ፴፩ - ፵፮

አቡሆሙ ለእለ አልቦሙ ነውር ወይሰምዕ ጸሎቶሙ ለንጹሓነ ልብ፤ ወያጸምዕ ስእለቶሙ ለእለ ኢያረ ምሙ ::

ነውር የሌለባቸው የቅዱሳን አባታ ቸው ነው፣ ልባቸው ንጹሕ የሆነ ሰዎችንም ጸሎት ይሰማል፣ ዝም የማይሉ ሰዎችንም ልመና ያዳም ጣል::

፳፤አኀድር እግዚኦ ሥምረተከ ላዕለ ኵሉ ፍጥረት እስመ አንተ ተአምር እምቅድመ ሕሊና ዘይ ሔሊ ልብ::

፳፤አቤቱ በፍጥረቱ ሁሉ ላይ ፈቃድህን አሳድር፣ ከአሳብ አስቀ ድመህ ልብ የሚያስበውን አንተ ታውቀለህና ::

፳፩፤ወኵሉ አጽናፈ ምድር የዐ ርጉ ለከ መሥዋዕተ ወዕጣነ በጸ ሎት ወበአኰቴት ::

፳፩፤የምድር ዳርቻዎች ሁሉም በጸሎትና በምስጋና መሥዋዕት ንና ዕጣንን ለአንተ ያሳርጋሉ::

፳፪፤ ዘሠርዐ መዋዕለ ይግበሩ ጽድቀ ወርኀው አናቅጸ ምሕረቱ ለኵሉ ለዘየኃሥሥ ኪያሁ ወመ ሀረነ ሕገ ወሥርዐተ ወአለበወነ ከመ ብዕለ ዝ ዓለም ኃላፊ ውእቱ ወሥነ ላህይ ኢይነብር ለዝሉፉ ወጽንዐ ኃያላን ትማስን ፍጡነ ::

፳፪፤ ጽድቅን ያደርጉ ዘንድ ዘመና ትን የሠራ እርሱ ነው፤እርሱንም ለሚሻ ሰው የቸርነቱ በር የተከ ፈተ ነው ፣ ሕግንና ሥርዓትንም አስተማረን፣ የዚህ ዓለም ሀብትም ኃላፊ እንደሆነ የመልክ ደም ግባትም ለዘለዓለም ጸንቶ እንደማ ይኖር፣ የኀይለኞች ብርታትም ፈጥና እንደምትጠፋ አስታወቀን ::

፳፫፤እስመ ቀደመ አብርሃም አቡነ ሐዊረ በፍኖተ ጽድቅ ወወሀብኮ ክብረ ወብዕለ ወበአሚን ፈጸመ ሕይወቶ ወትቤሎ አበዝኅ ዘርዐከ ከመ ኮከበ ሰማይ ወከመ ኆፃ ባሕር፣ ወወሀብኮ ይስሐቅሃ ባረኮ ወትቤሎ እሄሉ ምስለ ዘርእከ እምድኅሬከ፤ እስመ አእመርናሁ ከመ ለክርስቶስ ውእቱ ዘይቤሎ ከመዝ[፩]::

፳፫፤ አባታችን አብርሃም በጽድቅ መንገድ መሄድን ጀምሯልና፣ ክብርንና ሀብትን ሰጠኸው፣ ዘመ ኑንም በሃይማኖት ጨረሰ፣ ዘርህን እንደ ሰማይ ኮከብና እንደ ባሕር አሸዋ አበዛልሃለሁ አልኸው፣ ይስ ሐቅንም ሰጠኸው፣ እንዲህም ብለህ ባረክኸው፣ ከአንተም በኋላ ከዘርህ ጋር እኖራለሁ፣ እንዲህ ያለው ስለ ክርስቶስ እንደሆነ ዐውቀና ልና::

፩ ዘፍ. ፳፪: ፲፮-፲፰



፳፬፤ወለአቡነ ያዕቆብ ዘፈነውኮ ብሔረ ግብጽ ወትቤሎ ናሁ አነ እሄሉ ምስሌከ ወአብዝኆ አበዝኅከ ፈድፋደ::

፳፬፤አባታችን ያዕቆብንም ወደግ ብፅ የላክኸው አንተ ነህ፣ እነሆ ከአንተ ጋራ እኖራለሁ ፈጽሜም አበዛሃለሁ አልከው ::

፳፭፤ወከማሁ ትቤሎ ለሙሴ ቊል ዔከ ቅዱስ ወምእመን በኀበ ዕፀ ጳጦስ አነ ህልው እምቅድመ ዓለም ወይሄሉ ስምየ እስከ ለዓለም[፪]::

፳፭፤ ቅዱስና የታመነ ወዳጅህ ሙሴንም እንደዚሁ በቍጥቋጦው ዘንድ እኔ ከዓለም በፊት የነበርኩ ነኝ፣ ስሜም እስከ ዘለዓለም ይኖራል አልከው::

፳፮፤ወአንተሰ እግዚኦ ለዓለም ትነ ብር ወዝክርከኒ ለትውልደ ትውልድ[፫] ወባርክ ዘርዐ አብርሃም ይኩኑ ቡሩካነ እስከ ለዓለም::

፳፮፤አንተ ግን ለዘለዓለም ትኖራለህ ፣ መታሰብህም ለልጅ ልጅ ነው ፤ የአብርሃም ልጆችም እስከ ዘለዓለም የተባረኩ ይሆኑ ዘንድ ባርክ::

፳፯፤ፈጠርኮ ለሰብእ ይኩን ነባቤ ወአንተ ትቤ በጥበብከ ንግበር ሰብአ በአርአያነ ወበአምሳሊነ ወሤምኮ ለአዳም ይኩን መስፍነ ላዕለ ኵሉ ወወሀብኮ ሕይወተ ዘለዓለም::

፳፯፤ሰውን የሚናገር ይሆን ዘንድ ፈጠርከው፣ ሰውንም በመልካችን ንና በምሳሌያችን እንፍጠር ብለህ በጥበብህ ተናገርክ፣አዳምንም በሁሉ ላይ መስፍን አድርገህ ሾምከው፣ የዘለዓለም ሕይወትንም ሰጠኸው::

፳፰፤ወሶበ ዓለወ ትእዛዘከ አውፃ እኮ እምገነት ወአምጻእከ ላዕሌሁ ሞተ[፬]::

፳፰፤ትእዛዝህንም በአፈረሰ ጊዜ ከገ ነት አውጥተህ በእርሱ ላይ ሞትን አመጣህ::

፳፱፤ ወእምዝ ፈነውኮ ለዋሕድ ወልድከ ወአንሣእኮ እምድቀቱ ወአግባእኮ ውስተ ገነተ ትፍሥ ሕት::

፳፱፤ከዚህም በኋላ አንድ ልጅህን ልከህ ከውድቀቱ አነሣኸው፣ ደስታ ወደ አለበት ገነትም መለስከው::

፴፤ አንተ እግዚአብሔር ባሕቲ ትከ ዐቢይ ወኀያል ወግሩም መሓሪ ወየዋህ አኃዜ ኵሉ ዘትገብር መን ክረ ዘኢታርኅቅ ሣህለከ እምላዕለ ኵሉ ተግባሩ ወፍጥረቱ ኄር ወመ ፍቀሬ ሰብእ::

፴፤እግዚአብሔር ገናና ኃይለኛ የም ታስፈራ የምትምር የዋህ፤ ሁሉን የያ ዝህ፣ ድንቅን የምትሠራ፣ ከሥራ ውና ከፍጥረቱ ሁሉ ላይ ይቅርታ ህንም የማታርቅ፣ ቸርና ሰውን የምትወድ አንተ ብቻ ነህ::

፪ ዘፀ ፫: ፲፭
፫ መዝ ፻፩:፲፫-፲፬
፬ ዘፍ ፫ : ፳፪ - ፳፫

፴፩፤ ወትየውሆሙ ለኃጥኣን ወትመ ይጦሙ በብዝኀ ምሕረትከ።

፴፪፤ ወእንዘ ኢይደልወነ ናንቀዕዱ ኀቤከ ወናንሥእ አዕይንቲነ ውስተ ሰማይ አንተሰ ትኄጽር በጽንዐ ኀይ ልከ ዲበ ትሕትናነ ።

፴፫፤ ሰማይ ስቁል በትእዛዝከ ወም ድር ጸንዐት በቃልከ፣ እስመ ኃያል አንተ እግዚኦ ወጽድቅ ኵነኔከ መልዐ ምድረ ዘፈጠርከ።

## አንቀጽ ፴ወ፯

በእንተ ቅኄ ሠራዊት መንፈሳ ውያን ወቅድስት ቤተ ክርስቲያን፤

፩፤ ኵሎሙ ሠራዊተ መላእክት መንፈሳውያን ነደ እሳት እሙንቱ ወቅዱሳን ኪሩቤል ወሱራፌል እለ ፮ ክንፈሆሙ ኪያከ ይሴብሑ በዐቢይ ቃል ወይዜምሩ በቃል ዘኢያረምም ወይብሉ ቅዱስ ቅዱስ ቅዱስ እግዚ አብሔር ጸባኦት ፍጹም ምሉዕ ሰማ ያተ ወምድረ ቅድሳተ ስብሐቲከ፤

፪፤ ወኍልቆሙ ለእሙንቱ መላእ ክት ወሊቃነ መላእክት መናብርት ወሥልጣናት አጋዕዝት ወኃይ ላት ወሊቃናት ኪሩቤል ወሱራ ፌል፤ ይጸርሑ ወይብሉ ይትባ ረክ እግዚአብሔር አምላከ እስራኤል

፴፩፤ ኃጥአንን የዋህን ታደርጋለህ በቸ ርነትህም ብዛት ትመልሳቸዋለህ።

፴፪፤ እኛም ወደ አንተ አንጋጠን ዓይኖቻችንን ወደ ሰማይ አቅንተን እንመለከት ዘንድ ሳይገባን አንተ በኃይልህ ጽናት መዋረዳችንን ትመ ለከታለህ።

፴፫፤ ሰማይ በትእዛዝህ የተሰቀለ ነው፤ ምድርም በቃልህ ጸናች፣ ጌታ ሆይ አንተ ኃይለኛ ነህና፣ ፍርድህም እውነት ነውና የፈጠ ርከው ምድርን መላ ።

## ሠላሳ ሰባተኛ አንቀጽ

ስለ መንፈሳውያን መላእክትና ቤተ ክርስቲያን አገልግሎት ይናገራል፤

፩፤ የእሳት ነበልባል የሆኑ የረቂ ቃን መላእክት ሠራዊት ሁሉ ክን ፎቻቸው ስድስት የሚሆኑ ሱራ ፌልና ኪሩቤልም በታላቅ ቃል አን ተን ያመሰግናሉ፣ ዝም በማይል ቃልም ይዘምራሉ፣ ቅዱስ ቅዱስ ቅዱስ ፍጹም የሠራዊት ጌታ የጌ ትነትህ ምስጋና ሰማያትንና ምድ ርን የመላ ነው ይላሉ ።

፪፤ የእነዚያም መላእክትና የመላ እክት አለቆች ቁጥራቸው የወ ገን ስማቸው መላእክት መናብ ርት ሥልጣናት አጋዕዝት ኃይ ላት ሊቃናት ኪሩቤል ሱራፌል ይባላሉ፣ እየጮሁም የእስራኤል ፈጣሪ እግዚአብሔር ይመስገን ከአ ሕዛብ ወገን



ወቡርክት ዛቲ ቤተ ክርስቲያን እንተ አሕዛብ ትመስል ኀይለ ሰማያት መዓልተ ወሌሊተ በነፍስ ቅዱስ ወበልብ ንጹሕ ይዜምሩ ከመዝ ወይብሉ።

፫፤ ሠረገላሁ ለእግዚአብሔር ዕልፍ አእላፋት ወትእልፊተ አእላፋት ይሴብሕዎ ለእግዚአብሔር በደብረ ሲና ቅዱስ ሰማያት ወኵሉ ዘውስቴ ቶሙ ይገንዩ ለከ።

፬፤ እስመ አንተ ሰቀልኮ ለሰማይ ከመ ቀመር፤ ወሣረርካ ለምድር ወአጽናዕካ ዲበ ማይ።

፭፤ ወፈጠርከ ጽልመተ ወብርሃነ ወኍለቆሙ ለከዋክብት በምልያሙ ወሰመይኮሙ ለኵሎሙ በበአስማቲ ሆሙ ወኵሉ ፍጥረት ይዜንዉ ዕበ የከ ወዕፀወ ገዳምኒ አንተ አብ ቊልከ።

፮፤ ወበእንተዝ መፍትው ኵሉ ፍጥረተ ሰብእ የዐርጉ ለከ ስብሐተ ወአኰቴተ መሥዋዕተ ወቍርባነ ወዕጣነ በእግዚእነ ወመድኃኒነ ኢየ ሱስ ክርስቶስ ዋሕድ ወልድከ ።

፯፤ አንተ ውእቱ ባሕቲትከ አኃዜ ኵሉ ኄር ወመፍቀሬ ሰብእ ወገ ባሬ ሠናያት እስመ ለከ ስብሐት ወእኂዝ ለዓለመ ዓለም አሜን።

የምትሆን ቡርክት ቤተ ክርስቲያ ንም የሰማያት መላእክት ኃይልን ትመስላለች ይላሉ ሌሊትና ቀንም በልዩ ሰውነት በንጹሕ ልቡና እን ዲህ እያሉ ያመሰግናሉ ።

፫፤ የእግዚአብሔር ሠረገላው እልፍ አእላፋት የአእላፋት ትእልፊት በቅዱስ የሲና ተራራ እግዚአብ ሔርን ያመሰግኑታል፣ ሰማያትና በውስጣቸው ያለው ሁሉ አንተን ያመሰግናሉ።

፬፤ አንተ ሰማይን እንደ ዋልታ ሰቅለ ኸዋልና ምድርንም መሠረትሃት በውሃም ላይ አጽንተሃታልና።

፭፤ ጨለማንና ብርሃንን ፈጠርህ ከዋክብትንም በመላቸው ቈጠርሀ ቸው ሁላቸውንም በየስማቸው ጠራኻቸው፣ ፍጥረትም ሁሉ ገናና ነትህን ይናገራሉ፤ የዱር እንጨቶ ችንም አንተ አበቀልህ።

፮፤ ስለዚህም ነገር የሰው ፍጥረት ሁሉ ክብርንና ምስጋናን መሥዋ ዕትን፣ ቍርባንን፣ ዕጣንንም በአ ንድ ልጅህ በጌታችንና በመድኃ ኒታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ለአንተ ያሳርጉ ዘንድ አገባብ ነው ።

፯፤ ሁሉን የፈጠርክ ቸር ሰው ወዳጅ በጎ ነገርን የምታደርግ አንተ ብቻ ነህ፣ ለአንተ ክብርና ሥልጣን ይገ ባል ለዘለዓለሙ አሜን ።

፰፤ አንተ በሰማይ ወአንተ በምድር ወአንተ በባሕር ወአንተ ዘታስተጋብኦሙ ለኵሎሙ ፍጥረት እምአጽናፈ ምድር ወአልቦ ተፍጻሜት ለዕበይከ ::

፱፤እስመ አኮ ንሕነ ዘነበብነ ዘንተ አላ አንተ ትቤ አነ ውእቱ እግዚአብሔር አምላክ ዘመልዕልተ ሰማያት ወአነ ህልው ውስተ ኵሉ መካን ወአልቦ ባዕድ አምላክ ዘእንበሌየ[፩] ::

፲፤ እሙን ውእቱ ቃልከ ወአልቦ ዘይመስል ኪያከ እግዚአብሔር ቅዱስ እግዚኦሙ ለቅዱሳን ወነፍሰ ኵሉ ውስተ እዴከ ለከ ይደሉ ስብሐት ወልዕልና::

፲፩፤ዘኢይትዌለጥ መንበሩ ወኢይደክም ኃይሉ ወኢይትከሀል ዜንዎ ዕበዩ ወመንክር ሥነ ላህዩ::

፲፪፤ወአልቦ ዘይክል ቀሪበ ኀበ ማኅደሩ ወአልቦ ኍልቍ ለአእምሮ ጥበቡ ኢየኀልቅ ጽድቁ ወኢይጸሕቅ ዘይመክሮ ወኢየኀሥሥ ዘይረድኦ[፪] ::

፲፫፤አልቦቱ ጥንት ወኢተፍጻሜት ኢየኀልቅ መንግሥቱ ::

፰፤ በሰማይ አንተ ነህ፣ በምድርም አንተ ነህ፣ በባሕርም አንተ ነህ፣ ፍጥረትን ሁሉ ከምድር ዳርቻዎች የምትሰበስባቸው አንተ ነህ፣ ለገናንነትህ ፍጻሜ የለውም::

፱፤ ይህንንም የተናገርነው እኛ አይደለንም፤ ነገር ግን አንተ እኔ ከሰማዮች በላይ ያለሁ አምላክ እግዚአብሔር ነኝ፣ በቦታውም ሁሉ እኔ አለሁ፣ ያለ እኔም ሌላ አምላክ የለምአልህ::

፲፤ ቃልህም የታመነ ነው፤ የቅዱሳን ጌታቸው ቅዱስ እግዚአብሔር አንተን የሚመስል የለም፣ የሁሉ ነፍስም በእጅህ የተያዘ ነው፣ ለአንተ ክብርና ልዕልና ይገባል::

፲፩፤ ዙፋኑ የማይለወጥ ኃይሉም የማይደክም ነው፤ ገናንነቱን መናገር አይቻልም፤ የመልኩም ማማር ድንቅ ነው::

፲፪፤ ወደ ማደሪያውም መቅረብ የሚችል የለም፣ ለጥበቡ ዕውቀትም ቍጥርም የለውም፣ ጽድቁ አያልቅም፣ የሚመክረውም አይሻም፣ የሚረዳውም አይፈልግም::

፲፫፤ጥንት የለውም፣ ፍጻሜም የለው፣ መንግሥቱም አያልቅም::

፩ ዘዳግ ፬:፴፱
፪ ኢሳ ፵:፲፫



፲፬፤ ወአልቦ ዘይክል መዊኣ ኃይሉ ወአልቦሙ ኍልቍ ለሠራዊተ መላእክት ለእለ ይትለአክዎ ::

፲፭፤አንተ ውእቱ አቡሃ ለጥበብ ገባሬ ኵሉ ፍጥረት ወገባሪሃ ለሕግ ::

፲፮፤አንተ ታማስኖሙ ለዕልዋን ወትዔስዮሙ ለጻድቃን እግዚአብሔር አቡሁ ለእግዚእነ ወመድኃኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ እግዚኦሙ ለእለ ይገንዩ ሎቱ ወአልቦ ሐሰት በኀቤሁ ::

፲፯፤ ኢይነሥእ ህልያነ በውስተ ፍትሕ ወአልቦኍልቍ ለአኰቴቱ::

፲፰፤ ለከ ይደሉ ክብር ወስብሐት ወሰጊድ ዘያዐርግ ኀቤከ ኵሉ ነፍስ ነባቢ ለዓለመ ዓለም አሜን::

## አንቀጽ ፴ወ፰

በእንተ ከመ መፍትው ናዕርፍ ሰንበታተ ወናጽምዕ ቃለ መጻሕፍት ቅዱሳት::

፩፤ ከመ ንግበር ፈቃዶ ወንዘከር ሕማማቲሁ ዘገብረ በእንቲአነ እግዚአብሔር ቃል አኃዜ ኵሉ ዘፈጠረ ዓለመ በኢየሱስ ክርስቶስ መድኃኒነ::

፲፬፤ ኃይሉን ማቸነፍ የሚችለው የለም፣ለሚላኩት ሠራዊተ መላእክትም ቍጥር የላቸውም::

፲፭፤የጥበብ አባቷ አንተ ነህ፤ ፍጥረትን ሁሉ የፈጠርክ ሕግንም ሁሉ የሠራህ አንተ ነህ ::

፲፮፤ በእርሱ ዘንድ ሐሰት የሌለ፣ ለሚገዙለት ሰዎች ጌታቸው የሚሆን የጌታችንና የመድኃኒታችን የኢየሱስ ክርስቶስ አባቱ እግዚአብሔር አብ አንተ ወንጀለኞችን ታጠፋቸዋለህ፣ ለጻድቃንም ዋጋቸውን ትሰጣቸዋለህ::

፲፯፤በፍርድ መማለጃን አይቀበልም፤ ለምስጋናውም ቍጥር የለውም::

፲፰፤ የሚናገር ነፍስ ሁሉ ወዳንተ የሚያርግ አምላክ ሆይ ለአንተ ክብርና ምስጋና መስገድም ይገባል፣ ለዘለዓለሙ በእውነት ::

## ሰላሣ ስምንተኛ አንቀጽ

ሰንበቶችን ዕረፍት እናደርግ ዘንድ፣ የቅዱሳት መጻሕፍትንም ቃል እናደምጥ ዘንድ እንዲገባ ይናገራል::

፩፤ ፈቃዱን እንድናደርግና ሁሉን የያዘ ዓለምንሁሉ የፈጠረ መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ እግዚአብሔር ቃል ስለኛ ያደረጋቸውን መከራዎቹንም እናስብ ዘንድ እንደሚገባ ይናገራል::

፪፤ወሠርዐ ሰንበተ ወአዕረፈ ባቲ እምኵሉ ግብሩ ወለነኒ አዘዘነ ናዕርፍ እምኵሉ ግብረ እደዊነ ወንኩን ድልዋነ ለተቀንዮ ገቢረ ትእዛዛቲሁ ፩ ::

፫፤ወገብረ ለነ መዋዕለ በዓላት ፍሥሓ ለነፍሳቲነ ::

፬፤ወንዘከር ኪነ ጥበቡ ለዘሠምረ እግዚአብሔር ቃል ይትወለድ እምብእሲት በእንቲአነ ::

፭፤ ወአስተርአየ ገሀደ በዝ ግብር ወተጠምቀ ከመ ሰብእ እንዘ አምላክ ውእቱ ::

፮፤ ወተዐገሠ ሕማማተ መስቀል ወሞተ ወተንሥአ እሙታን በዐቢይ ኃይል።

፯፤ወበእንተዝ ንግበር ንሕነኒ በዓለ ዕለተ ትንሣኤሁ ቅድስት፤ወናክብር እሑደ ሰንበተ፤ወንሰብሕ ወንዘምር ለዘሞዖ ለሞት ወአብርሀ ኵሎ ዓለመ ወጸገወነ ክብረ ወስብሐተ ዘእንበለ ሙስና፤ ወአስተጋብአሙ ለዝርዋን ሕዝብ ወረሰዮሙ ይኩኑ ፩ መርዔተ ንጹሐ ወባረከ ላዕሌሆሙ ከመ ባረኮ ለእስራኤል።

፩ ዘፍ ፪ :- ፪ና፫

፪፤ሰንበትን ሠራ፣ከሥራውም ሁሉ አረፈባት፣እኛም ከእጆቻችን ሥራ ሁሉ እናርፍ ዘንድ ፣ ትእዛዛቱንም ለማድረግ ለአገልግሎት ሥራ ዝግጁዎች እንሆን ዘንድ አዘዘን ::

፫፤ ለሰውነቶቻችን ደስታም የበዓላት ቀኖችን ሠራልን ::

፬፤ ስለ እኛ ከሴት ይወለድ ዘንድ የወደደ የእግዚአብሔር ቃል የጥበቡን ብልሃት እናስባለን።

፭፤ በዚህም ሥራ ተገለጠ ፣አምላክም ሲሆን እንደ ሰው ተጠመቀ።

፮፤ የመስቀልንም መከራዎች ታገሠ፤ ሞተም ፤በታላቅ ኃይልም ከሙታን ተለይቶ ተነሣ።

፯፤ስለዚህም የቅድስት ትንሣኤውን ዕለት በዓል፣እናድርግ ፣እሑድ ሰንበትንም እናክብር፣ሞትን ድል ያደረገውን፣ዓለሙንም ሁሉ ያበራውን፣ያለ ጥፋትም ክብርንና ምስጋናን የሰጠንን ፣የተበታተኑትንም ሕዝብ የሰበሰባቸውንና አንድ ንጹሕ መንጋ ያደረጋቸውን፣ እስራኤልን እንደ ባረከው የባረካቸውን እናክብር እና መስግን።



፰፤ አንተ እግዚኦ ዘአውጻእኮሙ ለአበዊነ እምድረ ግብፅ ወባላህኮሙ እምቅኔ መሪር ወአድኀንኮሙ እምባሕር ወእምግብረ ግንፋል፪።

፱፤ ወአውጻእኮሙ እምትምልክተ ፈርዖን ወሠራዊቱ ወአኅለፍኮሙ ባሕረ እንተ የብስ ወሴሰይኮሙ በገዳም ኵሎ ሠናያተ ወሠራዕከ ሎሙ ሕገ ፲ተ ቃላተ ዘነበብከ በቃልከ ወዘጸሐፍከ በእዴከ።

፲፤ ወአዘዝኮሙ ያዕርፉ በዕለተ ሰንበት ከመ ይግነዩ ለከ ወይድኀኑ እምኵሉ እኩይ፫ ወአሠርኮሙ በቃለ ተግሣጽ።

፲፩፤ወአስተጋባእኮሙ ወአባእኮሙ ውስተ ቤተ መቅደስከ።

፲፪፤ወበእንተዝ አዘዘነ ናዕርፍ በኵሉ ሰንበት እስመ በዕለተ ሰንበት አዕረፈ እግዚእነ እምኵሉ ግብሩ፬ ::

፲፫፤ንኅሥሥ እንከ ኵሎ ሕጎ ወናእኵቶ ወንባርኮ ለእግዚአብሔር በእንተ ኵሉ ዘጸገወነ ሠናይቶ ለውሉደ ሰብእ ::

፲፬፤ወእምዝ ኵሉ ተዐቢ ትንሣኤሁ ቅድስት ዘመሀረነ እግዚእነ ወመድኀኒነ ወፈጣሪነ እግዚአብሔር ቃል ዘተወልደ እምቅድመ ይትፈጠር ዓለም እምአብ።

ዘፀ ፲፬: ፳፩-፴፩
ዘፀ. ፳.፰-፲
ዘፍ ፪.፪

፰፤ አቤቱ አባቶቻችንን ከግብፅ ምድር ያወጣሃቸው፤ከጽኑዕ አገዛዝም ነፃ ያደረግሃቸው፤ከባርነትና ጡብ ከመሥራትም ያዳንካቸው አንተ ነህ።

፱፤ከፈርዖንና ከሠራዊቱ አምልኮት አውጥተህ ባሕሩንም እንደ የብስ አሳለፍካቸው፤ በምድረ በዳም በጎውን ሁሉ መገብሃቸው ፤ በቃልህ የተናገርካቸውንና በእጅህ የጻፍካቸው የአሥሩ ቃላትንም ሕግ ሠራህላቸው።

፲፤ለአንተም ይገዙ ከክፋም ሥራ ሁሉ ይድኑ ዘንድ በሰንበት ቀን እንዲያርፉ አዘዝሃቸው ፣ በምክር ቃልም አንድ አደረግኻቸው ::

፲፩፤ሰብስበህም ወደ ቤተ መቅደስህ አገባሃቸው።

፲፪፤ስለዚህም በሰንበት ሁሉ እናርፍ ዘንድ አዘዘን፤ጌታችን በሰንበት ቀን ከሥራው ሁሉ አርፏልና።

፲፫፤እንግዲህ ሕጉን ሁሉ እንፈልግ ለሰው ልጆች ስለ ሰጠን መልካም ሁሉ እግዚአብሔርን እናክብረው እናመስግነው ::

፲፬፤ከዚህም ሁሉ ዓለም ሳይፈጠር ከአብ የተወለደ ጌታችንና መድኃኒታችን፣ ፈጣሪያችን እግዚአብሔር ቃል ያስተማረን ቅድስት ትንሣኤው ትበልጣለች።

፲፭፡ወተወልደ እማርያም ድንግል ዘእንበለ ትድምርት ሐመ ወተሰቅለ ወሞተ በመዋዕለ ጲላጦስ ጰንጤናዊ ወተንሥአ እሙታን በዕለተ ሰንበተ ክርስቲያን[፭] ::

፲፮፡ተዘከር እግዚኦ ዘናበውእ ለከ በዛቲ ዕለት መሥዋዕተ ወቍርባነ ወአኰቴተ ለስምከ ቅዱስ ለሠናይ ዕበየ ኀይልከ::

፲፯፡ወፈጸምከ ትንቢተ ወመሐርካ ለጽዮን ወተሣሃልካ ለኢየሩሳሌም ወአልዐልከ መንበሮ ለዳዊትገብርከ ማእከሌነ በልደተ ክርስቶስ ዘተወልደ እምዘርኡ በሥጋ እምድንግል[፮]::

፲፰፡አንተ እግዚኦ ተወከፍ ጸሎተ ወስዕለተ ሕዝብከ እለ ይጼውዑከ በጽድቅ በከመ ተወከፍኮሙ ለጻድቃን በበዘመኑ ::

፲፱፡ቀዳሚ ለአቤል ዘነጸርከ ላዕለ መሥዋዕቱ ወተወከፍከ[፯]::

፳፡ ወለኖኅ አመ ይወፅእ እምታቦት ወለአብርሃም አመ ይወፅእ እምብሔረ ከላውዴዎን[፰] ::

፳፩፡ወለይስሐቅ አመ ይወፅእ እምዐዘቅተ መሐላ ወለያዕቆብ በቤቴል ወለሙሴ በደብር ወለአሮን በገዳም ወለኢያሱ ወልደ ነዌ በገልገላ[፱]::

፭ ዮሐ ፲፱ ፲፬ - ፲፭
፮ ሮሜ ፩:፩-፭
፯ ዘፍ ፬ ፬
፰ ዘፍ. ፰ ፲፭
፱ ዘፍ. ፳፮. ፳፪.፣ኢያ. ፭. ፲. ፲፩

፲፭፡ከድንግል ማርያምም ያለሩካቤ ተወለደ ፤ በጰንጤናዊው በጲላጦስ ዘመንም ታመመ ፤ ተሰቀለ፤ ሞተም፣ በክርስቲያን ሰንበት ቀንም ከሙታን ተለይቶ ተነሣ::

፲፮፡አቤቱ በዚህች ቀን የምናቀርብልህን መሥዋዕትና ቊርባን ለቅዱስ ስምህና ለመልካም ገናና ኃይልህም የምናቀርበውን ምስጋና አስብ::

፲፯፡ትንቢትንም ፈጽመህ፣ ለጽዮን አዘንክላት፤ ኢየሩሳሌምንም ይቅር አልሃት፤ ከልጁ ከድንግል በሥጋ በተወለደ በክርስቶስ ልደትም የወዳጅህን የዳዊትን ዙፋን በኛ መካከል ከፍ ከፍ አደረግህ ::

፲፰፡አቤቱአንተ በየዘመኑ ጻድቃንን እንደተቀበልካቸው በእውነት የሚጠሩህ የሕዝብህን ልመናና ጸሎት ተቀበል::

፲፱፡መጀመሪያ የአቤልን መሥዋዕት ተመልክተህ ተቀበልህ ::

፳፡ ኖኅ ከመርከብ በወጣ ጊዜ ፤ አብርሃምም ከከላውዴዎን በወጣ ጊዜ ::

፳፩፡ ይስሐቅም ከመሐላ ጒድጓድ በወጣ ጊዜ ያዕቆብም በቤቴል፣ ሙሴን በተራራ፣አሮንንም በምድረ በዳ የነዌ ልጅ ኢያሱንም በገልገላ፣ ተቀበልህ ::



፳፪፡ ወለጌዴዎን በዲበ ኰኵሕ፣ ለማኑሄ ወብእሲቱ እንትኩይ ወለሶምሶን ሶበ ይጸምእ እምቅድመ የብስ፣ወለዮፍታሔበውስተቀትል፤ ወለባርቅ ወዲቦራ ላዕለ ሲሣራ፣ ወለሳሙኤል በመሴፋ[፲] ::

፳፫፡ ወለዳዊት በውስተ ገራህተ ኦርና ኢያቡሳዊ ወለሰሎሞን በገባዖን ዘኢየሩሳሌም፤ወለኤልያስ በደብረ ቀርሜሎስ፤ ወለኤልሳዕ በኀበ አንቅዕት[፲፩]::

፳፬፡ ወለኢዮሳፍጥ በውስተ ጸብእ ወለሕዝቅያስ በውስተ ደዌሁ ወዲበ ሰናክሬም[፲፪]::

፳፭፡ወለምናሴ በደብረ ከለዳውያን (ከላውዴዎን) እምድኅረ አበሰ[፲፫]::

፳፮፡ ወለኢዮስያስ በፓሳ[፲፬]::

፳፯፡ ወለዕዝራ አመ ይትመየጥ እምፄዋዌ[፲፭]::

፳፰፡ወለዳንኤል በግበ አናብስት[፲፮] ::

፳፱፡ወለዮናስ በውስተ ከርሠ አንበሪ[፲፯]::

፴፡ወለሠለስቱ ደቂቅ በውስተ ዕቶነ እሳት[፲፰]::

፴፩፡ ወለሐና በደብተራ ስምዕ በውስተ ታቦት[፲፱]::

፲ መሳ ፲፫- ፲፬-፲፭
፲፩ ፪ ነገሥ. ፪. ፲፬፤ዜና፡ መዋ. ቀዳ. ፳፩.፲፭
፲፪ ፪ኛ ዜና.መዋ.፴፪-፳-፳፬
፲፫ ፪ ዜና መዋ. ፴፬-፳፰-፳፱
፲፬ ፪ ዜና መዋ.፴፭-፲፰
፲፭ ዕዝራ. ፯- ፮
፲፮ ዳን. ፮-፳፬
፲፯ ዮናስ. ፪-፲፩
፲፰ ዳን. ፫. ፺ - ፺፩
፲፱ ፩ ሳሙ. ፩. ፲፱-፳

፳፪፡ጌዴዎንን በጭንጫ ላይ፣ማኑሄንና ሚስቱን እንትኩይንም፣ሶምሶንንም አስቀድሞ በደረቁ ቦታ በተጠማ ጊዜ፤ ዮፍታሔንም በውጊያ ጊዜ፤ባርቅንና ዲቦራንም በሲሳራ ላይ፤ሳሙኤልንም በመሴፋ ፤

፳፫፡ዳዊትን በኢያቡሳዊው በኦርና እርሻ ፣ሰሎሞንንም በኢየሩሳሌም በገባዖን ፣ኤልያስንም በቀርሜሎስ ተራራ፣ኤልሳዕንም በምንጮች ዘንድ::

፳፬፡ኢዮሳፍጥን በጦር ጊዜ፣ሕዝቅያስንም በደዌው በሰናክሬምም ላይ::

፳፭፡ምናሴንም ከበደለ በኋላ በከላውዴዎን ተራራ::

፳፮፡ኢዮስያስንም በፓሳ::

፳፯፡ዕዝራንም ከፄዋዌ በተመለሰ ጊዜ ::

፳፰፡ዳንኤልንም በአንበሶቹ ጉድጓድ::

፳፱፡ ዮናስንም በዓሣ አንበሪ ሆድ ውስጥ::

፴፡ሠለስቱ ደቂቅንም በእሳት ጉዳጓድ ውስጥ::

፴፩፡ሐናንም በምስክሩ ድንኳን በታቦት ውስጥ::

፴፪፤ ወለነህምያ አመ የሐንፅ ጥቅመ ምስለ ዘሩባቤል[፳]።

፴፫፤ ወለማትያን ምስለ ደቂቁ ውስተ ማዕዘንት።

፴፬፤ወለኢያኤል በዲበ በረከት።

፴፭፤ወይእዜኒ ከማሁ ተወከፍ ጸሎ ቶሙ ወስእለቶሙ እለ ያበ ውኡ ኀቤከ በአእምሮ በኢየሱስ ክርስቶስ።

፴፮፤ነአኵተከ በእንተ ኵሉ ግብር አኃዜ ኵሉ ኢታርኅቅ እምኔነ ሣህ ለከ ወምሕረተከ እስመ አንተ መሐሪ ወመስተሣህል ለኵሉ ትው ልደ ትውልድ።

፴፯፤ ዘተወከፍኮሙ ለሄኖስ ወለሄ ኖክ ወለኖኅ ወበመዋዕለ ሙሴ ወኢያሱ ወመሳፍንት።[፳፩]

፴፰፤ወበመዋዕለ ሳሙኤል ወኤል ያስ ወባዕዳን ነቢያት።

፴፱፤ ወበመዋዕለ ዳዊት ወካልኣን ነገሥት።

፵፤ ወበመዋዕለ አስቴር ወመርዶ ክዮስ ወበመዋዕለ ዮዲት ወበመዋ ዕለ ይሁዳ ወመቃብዮስ ወአ ኃዊሁ።[፳፪]

፵፩፤ ወለነኒ ከማሁ ተወከፍ በመ ዋዕሊነ።

፴፪፤ ነህምያንንም ከዘሩባቤል ጋራ ግንብን በሠራ ጊዜ።

፴፫፤ ማትያንንም ከልጆቹ ጋራ በማ ዕዘንት ውስጥ።

፴፬፤ኢያኤልንም በበረከት ላይ።

፴፭፤ዛሬም እንደዚሁ በዕውቀት ወዳንተ የሚያቀርቡትን ጸሎታቸ ውንና ልመናቸውን በኢየሱስ ክር ስቶስ ተቀበል ።

፴፮፤ ሁሉን የፈጠርክ ሆይ ! ስለ ሥራው ሁሉ እናመሰግንሃለን፤ ይቅርታህንና ምሕረትህን ከእኛ አታርቅ፤ አንተ ለልጅ ልጅ ሁሉ መሓሪና ይቅር ባይ ነህና።

፴፯፤ ሄኖስንና ሄኖክን ፤ ኖኅንም የተቀበልካቸው በሙሴና በኢያሱ በመሳፍንትም ዘመን።

፴፰፤ በሳሙኤልና በኤልያስ በሌ ሎችም ነቢያት ዘመን።

፴፱፤በዳዊትና በሌሎችም ነገሥታት ዘመን ።

፵፤በአስቴርና በመርዶክዮስ ዘመን፤ በዮዲትዘመን፤በይሁዳና በመቃቢስ በወንድሞቹም ዘመን።

፵፩፤ለእኛም በዘመናችን እንደዚሁ ተቀበል ።

[፳] ነህምያ፡ ፫-፲፮
[፳፩]. ዘፍ- ፮- ፳፫
[፳፪]. አስቴር-፱-፳፭-፳፮



፵፪፤ በዐቢይ ሊቀ ካህናት ኢየሱስ ክርስቶስ ወልድከ ዘአድኃንከነ እመ ጥባሕት ወረኃብ ወሴሰይከነ ወአጽ ገብከነ ወፈወስከነ እምደዌ ልሳናት እኩያን፤ወሠወርከነ እምኔሆሙ።

፵፫፤ኪያከ ነአኵት ኵሎ ጊዜ በኢየ ሱስ ክርስቶስ ዘጸጎከነ ቃለ ጥዑመ ወነባቤ፤ወልሳነ ሠናየ ከመ ቃለ አር ጋኖን ወረሰይከነ ንፍልጥ ጥዑመ ወመሪረ።

፵፬፤ዐይነ ለርእይ ወእዝነ ለሰሚዕ ወአንፈ ለአጼንዎ ወእደ ለገሢሥ ወእግረ ለሐዊር ወዘንተ ፈጠርከ በንስቲት ነጠብጣብ ዘይትዐቄር ውስተ ማኅፀን ወጸጎከ ነፍስ እንተ ኢትመውት ወረሰይኮ ይኩን ብእሴ ብሩህ ወገሠጽኮ በሕግከ ወአሠርገውኮ በትእዛዛቲከ ።

፵፭፤ወእምድኅረ ኅዳጥ መዋዕል ረሰ ይኮ መዋቴ ወጸገውኮ ትንሣኤ።

፵፮፤ ምንተ እንከ የዐሥየከ ሰብእ ዘገበርከ ሎቱ ዘንተ ኵሎ።

፵፯፤ወይእዜኒ መፍትው ለነ ናእኵ ትከ ወንሰብሕከ በአምጣነ ኃይልነ ወተወከፍ ጸሎተነ ይኩን ሥሙረ በኀቤከ።

፵፪፤ በገናናው ሊቀ ካህናት በል ጅህ በኢየሱስ ክርስቶስ ከሾተልና ከረኃብ አዳንኸን መገብኸን፤ አጠገ ብኸንም ፤ ከክፉዎች አንደበቶች ደዌም ፈወስከን ከእርሱም ሰወ ርኸን።

፵፫፤ ሁለጊዜም አንተን እናመስግ ናለን፤እንደ በገና ቃል ያማረ አንደበ ትንና የሚያናግር ጣዕም ያለው ቃልን በኢየሱስ ክርስቶስ ሰጠኸን ፤ ጣፋ ጭና መራራን እንድንለይ አደረግ ኸን።

፵፬፤ዓይንን ለማየት፤ጆሮን ለመስ ማት፤አፍንጫን ለማሽተት፤ እጅን ለመዳሰስ፤እግርን ለመኼድ፤ ይህን በማኅፀን በሚቋጠር በትንሽ ነጠ ብጣብ ፈጠርኽ፤ የማትሞት ነፍስ ንም ሰጠህ፤ ብሩህ ሰውም ይሆን ዘንድ አደረግኸው ፤ በሕግህም መከርከው፤ በትእዛዞችህም አስጌጥ ኸው።

፵፭፤ከጥቂትም ዘመን በኋላ የሚ ሞት፤ አደረግኸው ፤ ትንሣኤንም ሰጠኸው።

፵፮፤እንግዲህ ይህን ሁሉ ያደረግ ህለት ሰው ምን ይሰጥሃል?

፵፯፤ ዛሬም በተቻለን መጠን እና መሰግንህ እናከብርህ ዘንድ ለኛ አገባብ ነው፤ በአንተ ዘንድም የተ ወደደ ይሆን ዘንድ ጸሎታችንን ተቀበል ።

፴፰፡ወአድኀነነ እማዕሌቶሙ ለእለ ቦሙ ብዝኀ አማልክት ወባልሐነ እምእለ ይትቃረንዎ ለኢየሱስ ወአ ንግፈነ እምስሕተቱ ለሰይጣን ፡ እስመ አንተ ፈነውኮ ለኢየሱስ ክርስቶስ ፍቁር ወልድከ ይኩን ሰብአ እንዘ አምላክ ውእቱ::

፴፱፡ወአኅደርከ ላዕሌነ ጳራቅሊ ጦስሃ ወረሰይኮሙ ለመላእክት ይባ ርኩነ ወአኅሠርኮ ለሰይጣን እስመ ፈጠርከነ ወወሀብከነ ሕይወተ::

፵፡ዕቀበነ እንከ፡ ወሀበነ ሲሳየነ ፡ ወሚጠነ ውስተ ንስሓ እስመ ለከ ይደሉ ስብሐት ወሰጊድ በኵሉ ዘገበርከ ለነ በወልድከ መድኀኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ ለዓለመ ዓለም አሜን::

፵፩፡ ዘንተ ትልዉ አኃዊነ ኵሎ ጊዜ እግዚአብሔር የሀሉ ምስሌ ክሙ በዲበ ምድር ወበሰማያት ወበመንግሥተ አቡሁ ዘፈነዎ ያግ ዕዞ ለአዳም እምቅኔሁ ለሰይጣን::

፵፪፡ወሀበ ሕይወተ ለውሉደ ሰብእ ለእለ የአምኑ በእግዚአብሔር አም ላክ ፈጣሪ ከመ ይሕየዉ እለ የአ ምኑ በክርስቶስ ::

፵፫፡አየ አኰቴተ ዘይደሉ ናዓርግ ለእግዚአብሔር አብ በኢየሱስ ክር ስቶስ::

፴፰፡ብዙ ጣዖቶች ከአሏቸው ወንጀ ለኞችም አድነን፡ጌታችን ኢየሱስ ንም ከሚቃወሙት ታደገን፡ ከሰይ ጣንም ስሕተት አስጥለን፡ አምላክ ሲሆን ሰው ይሆን ዘንድ የወደደ ተወዳጁን ልጅህን ኢየሱስ ክርስቶ ስን ልከኸዋልና::

፴፱፡ ጳራቅሊጦስን በእኛ ላይ አሳ ደርህ፣ መላእክትንም እንዲባርኩን አደረግኻቸው፣ሰይጣንን ግን አዋ ረድኸው፣እኛን ፈጥረህ ሕይወትን ሰጥተኸናልና::

፵፡እንግዴህ ጠብቀን ፡ ምግባች ንንም ስጠን ፡ ወደ ንስሐም መል ሰን ፡ ባደረግህልን ሁሉ በልጅህ በመድኃኒታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ምስጋናና ስግደት ለአንተ ይገባልና ለዘለዓለሙ አሜን::

፵፩፡ ወንድሞቻችን ሆይ ሁለጊዜ ይህን ተከተሉ፡ እግዚአብሔር በምድር ላይና በሰማዮች አዳምን ከሰይጣን አገዛዝ ነፃ ያወጣው ዘንድ በላከው በአባቱ መንግሥ ትም ከእናንተ ጋር ይሁን ፡

፵፪፡በክርስቶስ ያመኑ ይድኑ ዘንድ ፈጣሪአምላክ በሚሆን በእግዚአብ ሔር ለሚያምኑ የሰው ልጆች ሕይወትን ሰጠ::

፵፫፡በኢየሱስ ክርስቶስ ለእግዚአብ ሔር አብ የሚገባ ምን ምስጋናን እናቀርባለን ?



፵፬፡ናሁ አቅደምነ ነጊሮተክሙ ወመሀርናክሙ ትዕቀቡ ዘንተ ኵሎ ከመ ትርከቡ ሕይወተ ዘለዓለም አሜን ::

## አንቀጽ ፴ወ፱

በእንተ ንዑሰ ክርስቲያን እለ ይፈ ቅዱ ይጠመቁ ::

፩፡ እስመ ለዘይፈቅድ ይጠመቅ መፍትው ይምሀርዎ ቃለ ተግ ሣጽ፣ ወያለብውዎ አእምሮ እግዚ አብሔር አብ፣ ወያጠይቅዎ ትስብ እተ ዋሕድ ወልድ ወሥምረተ መንፈስ ቅዱስ::

፪፡ወዓዲ ይንግርዎ ከመ ፈጠረ እግ ዚአብሔር ዓለመ ወሰብአ ዲቤሃ፣ ወዘከመ ኰነኖሙ እግዚአብሔር ለእኩያን በማየ ዓይኅ ወአጥፍ ኦሙ ለኃጥአን በእሳት ወአዕበ ዮሙ ለቅዱሳን በኵሉ ትውልደ ትውልድ ::

፫፡እሉ እሙንቱ ሴት ወሄኖስ፡ ወሄኖክ ፡ወኖኅ ወአብርሃም ወኵ ሎሙ እለ ተወልዱ እምኔሆሙ፡ ወመልከ ጼዴቅ ፡ ወኢዮብ ፡ ወሙሴ ወኢያሱ ፡ ወካሌብ ፡ ወፊንሐስ ካህን::

፬፡ወኵሎሙ ጻድቃን በበትውልዶ ሙ ወዘከመ መሀሮሙ ወኃረዮሙ እግዚአብሔር ለትዝምደ ሰብእ ወኢመነኖሙ::

፵፬፡ እነሆ አስቀድመን ነግረናች ኋል ፡ የዘለዓለም ሕይወትንም ታገኙ ዘንድ ይህን ሁሉ እንድት ጠብቁ አስተምረናችኋል::

## ሠላሳ ዘጠነኛ አንቀጽ

ይጠመቁ ዘንድ ስለሚወድዱ ንዑሰ ክርስቲያን ይናገራል::

፩፡ለሚጠመቅ ሰው የምክር ቃልን ያስተምሩት፡ እግዚአብሔር አብን ማወቅንም ልብ ያስደርጉት ፣የአን ድያ ልጁን ሰው መሆንና የመንፈስ ቅዱስን ፈቃድ ያስረዱት ዘንድ ይገባል::

፪፡ዳግመኛም እግዚአብሔር ዓለ ምንና በእርሷም ላይ ሰውን እንደ ፈጠረ፣ እግዚአብሔርም ክፉዎችን በማየ አይኅ እንደ ቀጣቸው፣ ኃጥ አንንም በእሳት እንደ አጠፋቸው፣ ቅዱሳንንም በልጅ ልጅ ሁሉ ከፍ እንዳደረጋቸው ይንገሩት ::

፫፡ እሊህም ሴት፣ ሄኖስ፣ ሄኖክ፣ ኖኅ፣ አብርሃም ፣ ከነሱ የተወለዱ ሁሉ መልከ ጼዴቅ ፣ ኢዮብ፣ ሙሴ ፣ ኢያሱ ፣ ካሌብ ፣ ካህኑ ፊንሐስም ናቸው ::

፬፡ሁሉም በየትውልዳቸው ጻድቃን ናቸው ፡ እግዚአብሔርም የሰው ልጆችን ፣ እንዳስተማራቸው እንደመረጣቸውና እንዳልናቃቸው ይንገ ሩት::

፭፤አላ ዳዕሙ ጸውፆሙ ወሚ
ጠሙ እምስሕተት ኵሎ ጊዜ ወእ
ምከንቱ ውስተ ዘበአማን አእምሮ።

፮፤ወአውጽኦሙ እምተቀንዮ ለጸ
ላኢ ወረሰዮሙ ሐራ ለገቢረ ትእ
ዛዙ ወአድኀኖሙ እምስሕተተ
ሞት ወመርሖሙ ውስተ ሕይ
ወት።

፯፤ይለቡኬ ዘንተ ኵሎ ዘይፈቅድ
ይጠመቅ ፤ ወይንሣእ ጥምቀተ።

፰፤ወዘሂ ያነብር እደ ላዕሌሁ
ይስግድ ለእግዚአብሔር አብ ገባሬ
ኵሉ ዘፈነወ ኀቤነ ወልዶ ዋሕደ
ኢየሱስሃ ክርስቶስሃ ያድኀኖሙ
ለትዝምደ ሰብእ እምርስሐተ ሥጋ
ወመንፈስ።

፱፤ወይቀድሶሙ በሥምረተ ኂሩቱ
ወይምርሖሙ ፍኖተ ወያብርህ አዕ
ይንተ አልባቢሆሙ ከመ ይለብዉ
መንክራቲሁ ።

፲፤ ወይትመሀሩ ጽድቆ ወይርኀቁ
እምዐመፃ ወይሑሩ ፍኖተ ርት
ዕተ ከመ ይኩኑ ድልዋነ ለተጠ
ምቆ ዳግም ልደት ውሉደ ክርስቶስ
በተስፋ ዘምሉዕ ጸጋ ወጽድቀ።

፲፩፤ ወእሙንቱሰ ይለብዉ ጥበበ
ወአእምሮ ወይትወከፉ ምግባረ
ጽድቅ ከመ ይባኡ ውስተ ሕይ
ወት ፤ ወእምድኅረ አኰቴት
ይምሀርዎሙ ትስብእቶ ለእግዚእ
ወሕማማቲሁ ወትንሣኤሁ እሙ
ታን ወዕርገቶ ውስተ ሰማይ ።

፭፤ነገር ግን ጠራቸው ፤ሁልጊዜ
ከስሕተትና ከጣዖት ወደ እውነ
ተኛ ዕውቀት መለሳቸው።

፮፤ለጠላት ከመገዛትም ነፃ አወጣ
ቸው ፤ትእዛዙንም ለመሥራት
ጭፍራን አደረጋቸው፤ከሞት ስሕ
ተትም አዳናቸው፤ ወደ ሕይወትም
መራቸው።

፯፤ይጠመቅ ዘንድ የሚወድ ይህን
ሁሉ አስተውሎ ጥምቀትን ይቀ
በል።

፰፤ እጁንም በላዩ የሚጭንበት
ከሥጋና ከመንፈስ ርስሐት ያድ
ናቸው ዘንድ አንድ ልጁን ኢየሱስ
ክርስቶስን ወደ እኛ ለላከ ሁሉን
ለፈጠረ ለእግዚአብሔር አብ ይስ
ገድ።

፱፤በቸርነቱ ፈቃድም ይቀድሳ
ቸው፤ መንገዱንም ይምራቸው ፤
ተአምራቱንም ያስተውሉ ዘንድ
የልቡናዎቻቸውን ዓይኖች ያብራላ
ቸው።

፲፤ጽድቁንም ይማሩ፤ ከበደልም
ይራቁ ፤ጸጋንና ጽድቅን በተመላ
ተስፋ የክርስቶስ ልጆች ለዳግም
ልደት ለመጠመቅ የተዘጋጁ ይሆኑ
ዘንድ፤የቀናች መንገድን ይሒዱ።

፲፩፤እሊኽውም ጥበብንና ዕውቀ
ትን ያስተውሉ፤ ወደ ሕይወትም
ይገቡ ዘንድ የጽድቅ ሥራን ይቀ
በሉ ፤ ከምስጋናም በኋላ የጌታን
ሰው መሆን መከራዎቹንና ከሙ
ታን መነሣቱን ወደ ሰማይም ማረ
ጉን ያስተምሯቸው ።





፲፪፤ ዘይፈቅድ ንኡሰ ክርስቲያን
ይጠመቅ ይምሀርዎ ያውግዝ ሰይ
ጣነ ወይእመን በክርስቶስ ወይኅ
ድግ ዘትካት ልማዶ ወያንጽሕ
ልቦ እምኵሉ እኩይ ወቂም ወር
ኵስ ወጽልሑት ወእምዝ ይትመ
ጠው ምሥጢራተ ቅድሳት።

፲፫፤ ከመ ብእሲ ጠቢብ ዘያነጽሕ
ሦከ ወአሜከላ እምገራህቱ ወይዘ
ርእ ውስቴቱ ሥርናየ።

፲፬፤ወከማሁ አንትሙኒ መፍትው
ትትገኀሡ እምኵሉ ርኵስ ወታን
ጽሑ አልባቢክሙ እምእኩይ ከመ
ትኩኑ ድልዋነ ለተጠምቆ በቅድ
ስት ጥምቀት ።

፲፭፤እስመ ከመዝ መሀረነ እግዚ
እነ እንዘ ይብል አጥምቅዎሙ
ለኵሎሙ በስመ አብ ወወልድ
ወመንፈስ ቅዱስ ።

፲፮፤ወካዕበ የአዝዝዎ ለዘይጠመቅ
ይበል ከመዝ፤ አወግዘከ ሰይጣን
ወኵሎ ምግባራቲከ፤ ወኵሎ እከ
የከ ወኵሎ ቅኔከ ፤ወኵሎ መላእክ
ቲከ፤ወኵሎ መናግንቲከ ፤ወኵሎ
ኃይለከ ።

፲፯፤ወእምድኅረ ግዘት ይትአመን
ወይበል ፤ አአምን በክርስቶስ ወካ
ዕበ አአምን ወእጠመቅ በ፩ አም
ላክ ዘበአማን ዘኢተወልደ አቡሁ
ለእግዚእነ ወመድኃኒነ ኢየሱስ
ክርስቶስ አኃዜ ኵሉ ወፈጣሬ
ኵሉ ዘእምኔሁ ኵሉ ኮነ።

፲፪፤ሊጠመቅ የሚወድ ንዑስ ክር
ስቲያንም ሰይጣንን ያውግዝ ፤
(እክህደከ ሰይጣን ይበል) በክርስቶ
ስም ይመን፤ የቀደመ ልማዱንም
ይተው ፤ ልቡንም ከክፉ ሕሊና፤
ሁሉና ከቂም ከርኵሰትና ከሽንገላ
ያንጻ ፤ከዚህም በኋላ ሥጋውንና
ደሙን ይቀበል ።

፲፫፤ከእርሻው እሾህንና ደንደርን
አንጽቶ በውስጡ ስንዴን እንደ
ሚዘራ ብልህ ሰው ይሁን።

፲፬፤ እናንተም እንደዚሁ ከርኩሰት
ሁሉ ትለዩ ዘንድ ከክፋትም ልቡና
ችሁን ታነጹ ዘንድ ፣ አገባብ ነው፤
በቅድስትጥምቀት ለመጠመቅ ዝግ
ጁዎችን ትሆኑ ዘንድ።

፲፭፤ጌታችን እንዲህ ብሎ አስተም
ሮናልና ሁሉን በአብ በወልድ በመ
ንፈስ ቅዱስ ስም አጥምቋቸው።

፲፮፤ዳግመኛም የሚጠመቀው ሰው
እንደዚህ ይል ዘንድ ይዘዙት፤ ሰይ
ጣን ሆይ እክድሃለሁ ፣ሥራዎችህን
ሁሉና ክፋትህን ሁሉ ፤ ግዛትህን
ሁሉ፤ መላእክቶችህን ሁሉ ተንኮ
ሎችህን ሁሉ፤ኃይልህን ሁሉ አወ
ግዛለሁ።

፲፯፤ከውግዘትም በኋላ አምኖ እን
ዲህ ይበል ፤ በክርስቶስ አምና
ለሁ ፤ዳግመኛም ሁሉ ከእርሱ በሆነ
ሁሉን በያዘና ሁሉን በፈጠረ በጌ
ታችንና በመድኃኒታችን በኢየሱስ
ክርስቶስ አባት ባልተወለደ እው
ነተኛ በሚሆን አንድ አምላክ አምኜ
እጠመቃለሁ።

፲፰፤ ወእጠመቅ በዋሕድ ወልዱ ኢየሱስ ክርስቶስ ዘተወልደ እምቅድመ ዓለም በሥምረተ አብ ዘቦቱ ኵሉ ኮነ፤ ዘበሰማይኒ ወዘበምድርኒ ዘያስተርኢ ወዘኢያስተርኢ፤ ወዘወረደ እምሰማያት በደኃሪ መዋዕል ወተሰብአ እማርያም እምቅድስት ድንግል፤ተወልደ በንጽሕ ወፈጸመ ሕገ አቡሁ፤ወተሰቅለ በእንተአነ በመዋዕለ ጲላጦስ ጶንጤናዊ ወሞተ፤ ወነበረ ውስተ ከርሠ ምድር ሠሉሰ መዋዕለ ወሠሉሰ ለያልየ፤ወተንሥአ እሙታን ወዐርገ ሰማያተ በስብሐት ወነበረ በየማነ አብ፤ወካዕበ ይመጽእ በደኃሪ መዋዕል ይኰንን ሕያዋነ ወሙታነ ፤ ወአልቦ ማኅለቅት ለመንግሥቱ።

፲፰፤ቅድመ ዓለም በአባቱ ፈቃድ በተወለደ በአንድ ልጁ በኢየሱስ ክርስቶስ አምኜ እጠመቃለሁ፤በእርሱ ሁሉ ሆነ፤በሰማይና በምድር ያለው የሚታየውና የማይታየው፤ በኋለኛው ዘመን ከሰማየ ሰማያት ወረደ ፤ ከቅድስት ድንግል ማርያም ሰው ሁኖ በንጽሕና ተወለደ፤ የአባቱንም ሕግ ፈጸመ ፤ስለ እኛም በጶንጤናዊው ጲላጦስ ዘመንም ተሰቀለ፤ሞተ፤በከርሠ መቃብርም ሦስት መዓልትና ሦስት ሌሊት አደረ፤ከሙታን ተለይቶ ተነሣ፤በክብር ወደ ሰማያት ዐረገ፤በአብ ቀኝ ተቀመጠ፤ ዳግመኛም በኋላ ዘመን በሕያዋንና በሙታን ይፈርድ ዘንድ ይመጣል፤ ለመንግሥቱም ፍጻሜ የለውም ይበል።

፲፱፤ወዓዲ እጠመቅ በጰራቅሊጦስ መንፈስ ቅዱስ ዘወጽአ እምኀበ አብ ወጸንዐ በወልድ ወኀደረ በላዕሌሆሙ ለቅዱሳን አበው ቀደምት፤ ወካዕበ ተፈነወ ወተውህበ እምኀበ አብ ላዕለ ሐዋርያት በእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ፤ ወእምድኅረ ሐዋርያት ተፈነወ ወተውህበ ለመሃይምናን በቤተ ክርስቲያን እንተ ሐዋርያት ለሥርየተ ኀጢአት፤ወበመንግሥተ ሰማያት፤ወለሕይወት ዘይመጽእ ለዓለም።

፲፱፤ዳግመኛም ከአብ በሠረፀ በወልድም ህልውና በጸና በአጽናኙ በመንፈስ ቅዱስ አምኜ እጠመቃለሁ፤ እርሱም በቅዱሳን ቀደምት አባቶች ላይ አደረ፤ዳግመኛም ከአብ በጌታ በኢየሱስ ክርስቶስ ለሐዋርያት ተላከ ከሐዋርያት በኋላም በሐዋርያት ቤተ ክርስቲያን ኀጢአት ሥርየት በመንግሥተ ሰማያት፤ በሚመጣውም በዘለዓለም ለሚያምኑ ለምእመናን ተልኮ ተሰጠ።



፳፤ወእምድኅረ አምነ ይቅረብ ኀበ ቅብዐ ዘይት ቅዱስ ዘቀደስዎ ካህናት ለሥርየተ ኃጢአት።

፳፤ከአመነም በኋላ ኃጢአትን ለማስተሥረይ ካህናት ወደ አከበሩት ቅዱስ የዘይት ቅብዐት ይቅረብ።

፳፩፤ወይጸሊ ካህን ወይስአል ኀበ እግዚአብሔር ወይበል እግዚአብሔር አብ ዘኢተወልደ አቡሁ፤ ለእግዚእነ ወመድኀኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ ያንጽሖ ለዝንቱ ዘይት በስመ ዋሕድ ወልዱ ኢየሱስ ክርስቶስ።

፳፩፤ካህኑም ይጸልይ፤ ወደ እግዚአብሔር ይለምን፤እንዲህም ይበል፤ የጌታችንና የመድኃኒታችን የኢየሱስ ክርስቶስ አባት ያልተወለደ እግዚአብሔር አብ በአንድ ልጁ በኢየሱስ ክርስቶስ ስም ይህን ዘይት ያንጻው።

፳፪፤ይኩን አኰቴተ መንፈሳዌ ወኃይለ ለስርየተ ኀጢአት፤ ወአሚነ ለዛቲ ጥምቀት በቅብዐቱ ለዝንቱ ዘይት ቅዱስ ከመ ይኩን ድልወ ለዐቂበ ትእዛዝከ።

፳፪፤መንፈሳዊ ጸጋን ፤ ለኃጢአት ስርየትም ኀይልን ፤ ለዚች ጥምቀትም መታመኛን ይሁን፤ይህን ቅዱስ ዘይት በመቀባት ትእዛዝህን ለመጠበቅ የተዘጋጀ ይሆን ዘንድ።

## አንቀጽ ፵

## ዓርባኛ አንቀጽ

በእንተ ጸሎት ዘይትነበብ ዲበ ማይ።

በውሀ ላይ ስለሚጸለይ ጸሎት ይናገራል።

፩፤ሶበ ይቀውም ካህን ዲበ ማይ ከመዝ ይጸሊ እንዘ ይብል እግዚአብሔር አምላክነ አኃዜ ኵሉ አቡሁ ለዋሕድ ወልድከ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ አእኰተከ።

፩፤ ካህን በውሀ ላይ በቆመ ጊዜ እንዲህ እያለ ይጸልይ፤ የአንድ ልጅህ የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ አባት ሁሉን የፈጠረ አምላካችን እግዚአብሔር ሆይ አመሰግንሃለሁ።

፪፤ዘፈነውኮ ዋሕድ ወልድከ፤አድኀነ ኵሎ ዓለመ ወይሰምዕ ለኵሉ ዘለአሎ ወይሰብክ በእንተ መንግሥተ ሰማያት ወስርየተ ኃጢአት ወትንሣኤ ሙታን።

፪፤የላክኸው አንድ ልጅህ ዓለሙን ሁሉ አዳነ ፤ የለመነውንም ሁሉ ይሰማል፤ስለ መንግሥተ ሰማያት ስለ ኃጢአት ሥርየትና ስለ ሙታን መነሣት ያስተምራል ።

፫፤ እሴብሐከ ወአአኵተከ ወእቄድስከ እስመ ተዐገሥከ ሕማማተ ሞት በዲበ መስቀል በእንተ ኵሉ ዘጸጎከ ጥምቀተ ዘዳግም ልደት።

፬፤ እሴብሐከ እግዚአብሔር ኢየሱስ ክርስቶስ ወመንፈስ ቅዱስ ዘኢመነኖ ለትዝምደ ሰብእ ገባሬ ኵሉ መንክራት።

፭፤ ዘፈጠርኮ ለአዳም ወአንበርኮ ውስተ ገነት፤ ወሶበ ዐለወ ትእዛዘከ አውፃእኮ እምገነት በርቱዕ ፍትሕከ።

፮፤ ወበብዙኅ ምሕረትከ ኢገደፍከ አላ ፈነውኮ ለወልድከ በደኃሪ መዋዕል ይኩን ሰብአ ወይፁር ሕማመ ዘእንበለ ኀጢአት ።

፯፤ እስእለከ ወአስተበቊዐከ፤ ርኢ እምሰማይ ላዕለ ዝንቱ ማይ ወቀድሶ በኀይልከ ከመ ይኩኑ ኵሎሙ እለ ይጠመቁ እምኔሁ በትእዛዘ ክርስቶስ ይኩኑ ኅቡረ አዕርክቲሁ ምስሌሁ።

፰፤ በስቅለትከ ወበሞትከ ወበትንሣኤከ ወበዕርገትከ ውስተ ሰማይ ከመ ታድኅኖሙ እሞተ ኀጢአት ወይሕየዉ በጽድቅ ።

፱፤ ወእምድኅረዝ ያጥምቅ በስመ አብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ ወይቅባዕ በለሳነ ።

፫፤ አከብርሃለሁ ፣ አመሰግንሃለሁ፤ እቀድስሃለሁ፤የሁለተኛ መወለድ ጥምቀትን ስለ ሰጠኸው ሁሉ በመስቀል ላይ የሞት መከራዎችን ተአግሠሃልና።

፬፤እግዚአብሔር አብ ፤ ኢየሱስ ክርስቶስ ፤ መንፈስ ቅዱስም ሆይ አመሰግንሃለሁ የሰው ወገንን ያልናቅኸው ፣ ተአምራትን ሁሉ የሚሠራ ሆይ።

፭፤አዳምን ፈጥረህ በገነት ያኖርከው ትእዛዝህንም በአፈረሰ ጊዜ በቀና ፍርድህ ከገነት ያወጣኸው።

፮፤በብዙ ቸርነትህም አልጣልኸውም፤ነገር ግን በኋላ ዘመን ሰው ሁኖ ከኃጢአት በቀር መከራን ይቀበል ዘንድ ልጅህን ላክኸው ።

፯፤እለምንሃለሁ እማልድሃለሁ፤ ከሰማይ ሁነህ በዚህ ውሀ ላይ ተመልከት፤ በክርስቶስ ትእዛዝ በእርሱ የሚጠመቁ ከእርሱ ጋር በአንድነት ወዳጆቹ ይሆኑ ዘንድ በኃይልህ ቀድሰው ።

፰፤በስቅለትህና በሞትህ፤በትንሣኤህና ወደ ሰማይ በማረግህ፤ከኃጢአት ሞት ታድናቸውና በጽድቅ ይኖሩ ዘንድ ።

፱፤ከዚህም በኋላ በአብ በወልድ በመንፈስ ቅዱስ ስም ያጥምቅ ሜሮንንም





## አንቀጽ ፵ወ፩

በእንተ ጸሎት ላዕለ ሜሮን ዘይት ነበብ፤

፩፤እግዚአብሔር አብ አምላክ ፤ እግዚአ ኵሉ ፍጥረት ጸጎከ መዓዛ ዝንቱ ሜሮን ሠናየ ለኵሎሙ አሕዛብ እለ የአምኑ ብከ ወኀይለ ዝንቱ ሜሮን ምሥጢር ለእለ ይጠመቁ በስምከ ።

፪፤ወእምድኅረዝ ይቁም ወይጸሊ ዘንተ ጸሎተ ዘመሀረነ እግዚእነ አቡነ ዘበሰማያት እስከ ተፍጻሜቱ።

፫፤ወእምዝ ይትመየጥ ካህን መንገለ ምሥራቅ ወያንሥእ አዕይንቲሁ ውስተ ሰማይ ወይበል ሰብሕዎ ለእግዚአብሔር እስመ ኄር እግዚአብሔር ፣ ወዘምሩ ለስሙ እስመ ሠናይ፤እስመ ለዓለም ምሕረቱ።

## አንቀጽ ፵ወ፪

ከመዝ ይጸልዩ ዘንተ ጸሎተ ሐዲሳን እለ ተጠምቁ።

፩፤እግዚአብሔር አኃዜ ኵሉ አቡሁ ለእግዚእነ ወመድኃኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወልድ ዋሕድ መፍቀሬ ንጽሕት ሥጋ ዘይትዌከፍ ልበ የዋህ ወመንፈሰ ትሑተ ወአእምሮ ጥበብ እንተ አልባቲ ሙስና፤ ወመንፈሰከ ቅዱሰ ፈኑ ላዕሌነ በሥምረትከ

www.ethiopianorthodox.org

## ዓርባ አንደኛ አንቀጽ

በሜሮን ላይ ስለሚጸለየው ጸሎት ይናገራል።

፩፤ የፍጥረት ሁሉ ጌታ ፈጣሪ እግዚአብሔር አብ ሆይ ! አንተን ለሚያምኑ አሕዛብ ሁሉ በጎ የሚሆን የዚህን ሜሮን መዓዛ ሰጠህ፤ በስምህም ለሚጠመቁ የዚህን ሜሮን ምሥጢር ኃይል ሰጠህ።

፪፤ ከዚህም በኋላ ቁሞ ጌታችን ያስተማረንን ይህን ጸሎት አቡነ ዘበሰማያትን እስከ ፍጻሜው ይጸልይ።

፫፤ከዚህም በኋላ ካህኑ ወደ ምሥራቅ ተመልሶ ዓይኖቹን ወደ ሰማይ አቃንቶ እንዲህ ይበል፤ እግዚአብሔር ቸር ነውና እግዚአብሔርን አመስግኑት፤በጎም ነውና ለስሙ ዘምሩ፤ቸርነቱ ለዘለዓለም ነውና።

## ዓርባ ሁለተኛ አንቀጽ

አዲስ አማንያን ሲጠመቁ ይህን ጸሎት ይጸልዩ ዘንድ እንዲገባ ይናገራል ።

፩፤የአንድ ልጅህ የጌታችን የመድኃኒታችን የኢየሱስ ክርስቶስ አባት ንጽሕት ሥጋን የምትወድ ቅን ልብንና የተዋረደ መንፈስን፤ ጥፋት የሌለባት ጥበብን ማወቅንም የምትቀበል፤የሁሉ ፈጣሪ እግዚአብሔር ሆይ! በፈቃድህና በኃይልህ ብርታት ቅዱስ መንፈስን በእኛ ላይ ላክ ።

፬፥ በኢየሱስ ክርስቶስ ዘቦቱ ለከ ምስሌሁ ወምስለ ቅዱስ መንፈስ ስብሐት ወእኂዝ ለዓለመ ዓለም አሜን ።

## አንቀጽ ፶ወ፫

በእንተ ኤጲስ ቆጶሳት እለ ተሠይሙ በኀበ ሐዋርያት።

፩፥ ከመዝ ውእቱ አስማቲሆሙ ለእለ ተሠይሙ በኀቤነ ቀዳሚ በኢየሩሳሌም ያዕቆብ እንሁ ለእግዚእነ፥ወእምድኅሬሁ ተሠይመ ሀየንቴሁ ስምዖን ዘቀለዮጳ።

፪፥ወእምድኅሬሁ ይሁዳ ዘያዕቆብ፥ ወበቂሣርያ ዘፍልስጥኤም ቀዳሚ ዘኬዎስ መጸብሐዊ፥ወእምድኅሬሁ ቆርኔሌዎስ፥ወእምድኅሬሁ ቴዎፍሎስ ።

፫፥ወበአንጾኪያ ቀዳሚ አውድዮስ በኀበ ጴጥሮስ ወእምድኅሬሁ አግናጥዮስ በኀበ ጳውሎስ ።

፬፥ ወበእስክንድርያ ቀዳሚ አንያኖስ ዘተሠይመ በኀበ ማርቆስ ወንጌላዊ ፥ ወእምድኅሬሁ አውልዮስ በኀበ ሉቃስ ወንጌላዊ ።

፭፥ ወበቤተ ክርስቲያን ዘሮም ቀዳሚ ኤሌኖስ በኀበ ጳውሎስ፥ ወእምድኅሬሁ ቀሌምንጦስ ዘተሠይመ በኀበ ጴጥሮስ ።

፬፥በኢየሱስ ክርስቶስ በእርሱ ከእርሱና ከመንፈስ ቅዱስም ጋር ለአንተ ምስጋናና ሥልጣን ይገባል ለዘለዓለሙ አሜን ።

## ዓርባ ሦስተኛ አንቀጽ

በሐዋርያት ስለ ተሾሙ ኤጲስ ቆጶሳት ይናገራል።

፩፥ በእኛም ዘንድ የተሾሙ ስማቸው ይህ ነው፥መጀመሪያ በኢየሩሳሌም የተሾመ የጌታችን ወንድም ያዕቆብ ነው፥ ከእርሱም ቀጥሎ በእርሱ ፈንታ የቀለዮጳ ልጅ ስምዖን ተሾመ ።

፪፥ከእርሱም ቀጥሎ የያዕቆብ ልጅ ይሁዳ ነው፥ በፍልስጥኤም ቂሣርያም መጀመሪያ ቀራጩ ዘኬዎስ፥ ከእርሱም ቀጥሎ ቆርኔሌዎስ፥ከእርሱም ቀጥሎ ቴዎፍሎስ።

፫፥ በአንጾኪያም መጀመሪያ በጴጥሮስ የተሾመ አውድዮስ፥ ከእርሱም በኋላ በጳውሎስ የተሾመ አግናጥዮስ።

፬፥በእስክንድርያም መጀመሪያ በወንጌላዊ ማርቆስ የተሾመ አንያኖስ፥ ከእርሱም በኋላ በወንጌላዊው ሉቃስ የተሾመ አውልዮስ።

፭፥ በሮም ቤተ ክርስቲያንም መጀመሪያ በጳውሎስ የተሾመ ኤሌኖስ፥ ከእርሱም በኋላ በጴጥሮስ የተሾመ ቀሌምንጦስ።



፮፥ወበኤፌሶስ ቀዳሚ ጢሞቴዎስ በኀበ ጳውሎስ፥ወእምድኅሬሁ ዮሐንስ ዘተሠይመ በኀበ ዮሐንስ ወንጌላዊ ።

፯፥ወበእስምርናስ ቀዳሚ ርስጦስ፥ ወእምድኅሬሁ አስተራቴዎስ ዘሎይስ፥ወእምድኅሬሁ አርስጦን ።

፰፥ወበበርጋሞስ ቀዳሚ ጋይዮስ።

፱፥ወበፊላድልፍያ ቀዳሚ ድሜጥሮስ በኀበ ጴጥሮስ ።

፲፥ ወበክንክራኦስ ቀዳሚ ሉኪዮስ በኀበ ጳውሎስ ።

፲፩፥ወበቀርጤስ ቲቶ።

፲፪፥ወበአቴና ዲዮናስዮስ ።

፲፫፥ወበጥሪጶሊ ፎኒቅያ ማራሶን።

፲፬፥ወበሎዶቅያ አርካቦስ።

፲፭፥ ወበቈላስይስ ፊልሞና።

፲፮፥ወበበርያሶን ዘመቄዶንያ አናሲሞስ ዘፊልሞና።

፲፯፥ ወበቤተ ክርስቲያን ዘገላትያ ክሪስኪስ።

፲፰፥ በብሔረ እስያ አቂላ ወንኪትስ።

፲፱፥ ወበቤተ ክርስቲያን ዘኤጌና ቅርስጳስ።

፳፥ እሉ እሙንቱ እለ ተአመናሆሙ ወሤምናሆሙ በኢየሩሳሌም ወፈነውነ ይስብኩ ወይምሀሩ [illegible]

፮፥ በኤፌሶስም መጀመሪያ በጳውሎስ የተሾመ ጢሞቴዎስ ከእርሱም በኋላ በወንጌላዊው ዮሐንስ የተሾመ ዮሐንስ።

፯፥በእስምርናስም መጀመሪያ አርስጦስ፥ ከእሱም በኋላ የሎይስ ወገን አስተራቴዎስ፥ከእሱም ቀጥሎ አርስጦን ።

፰፥በበርጋሞስም መጀመሪያ የተሾመ ጋይዮስ።

፱፥በፊላድልፍያም መጀመሪያ በጴጥሮስ ዘንድ የተሾመ ድሜጥሮስ።

፲፥በክንክራኦስም መጀመሪያ በጳውሎስ ዘንድ የተሾመ ሉኪዮስ ።

፲፩፥በቀርጤስም ቲቶ ።

፲፪፥በአቴናም ዲዮናስዮስ ።

፲፫፥በጥሪጶሊ ፎኒቅያም ማራሶን።

፲፬፥በሎዶቅያም አርካቦስ።

፲፭፥በቈላስይስም ፊልሞና።

፲፮፥በመቄዶንያና በበርያሶን የፊልሞና ወገን አናሲሞስ።

፲፯፥በገላትያ ቤተ ክርስቲያን ክሪስኪስ።

፲፰፥በእስያ ሀገር አቂላና ንኪትስ።

፲፱፥በኤጌና ቤተ ክርስቲያንም ቅርስጳስ ።

፳፥ በኢየሩሳሌም አምነን የሾምናቸው በያገራቸው ይሰብኩ ያስተምሩ ዘንድ የላክናቸው እሊህ ናቸው።

፳፩ ፣ ለእሉኬ ተዘከሩ ፃማሆሙ ወተ ወከፉ ተግሣጾሙ ወዕቀቡ ቃሎሙ ፣ እግዚአብሔር የሃሉ ምስሌ ክሙ እምይእዜ ወእስከ ለዓለም።

፳፪ ፣ በከመ ይቤለነ አመ የዐርግ ሰማየ ኀበ አብ ናሁ አነ ምስሌክሙ በኵሉ መዋዕል እስከ ኅልቀተ ዓለም[፩]።

፳፫ ፣ ስብሐት ለእግዚአብሔር ዘሎቱ ስብሐት ወክብር ለዓለመ ዓለም አሜን ወአሜን ለይኩን ለይኩን።

፩ ማቴ. ፳፰. ፳

፳፩ ፣ የእነዚህን ድካማቸውን አስቡ ፣ ምክራቸውንም ተቀበሉ ፣ ቃላቸውንም ጠብቁ ፣ እግዚአብሔር ከእናንተ ጋር ይሁን ፣ ከዛሬ ጀምሮ እስከ ዘለዓለሙ።

፳፪ ፣ ወደ ሰማይ ወደ አብ በዓረገ ጊዜ ዓለም እስኪያልፍ ድረስ በዘመኑ ሁሉ እኔ ከእናንተ ጋራ ነኝ እንዳለን ።

፳፫ ፣ ጌትነትና ክብር ለዘለዓለሙ የእርሱ ገንዘብ ለሆነ ለእግዚአብሔር ምስጋና ይግባው አሜን ፣ አሜን ይሁን ይሁን።

## መጽሐፈ ቀሌሜንጦስ ዘሮም
## በግእዝና በአማርኛ

መጽሐፈ ቀሌሜጦስ ምድቡ ከሰማንያ አሀዱ (፹፩) ቅዱሳት መጻሕፍት ነው በ1958 ዓ.ም የታተመው ባለ አንድምታ ፍትሐነገሥት ከራእየ ዮሐንስ ቀጥለው የሚመደቡት አራት መጻሕፍተ ሲኖዶስ ሁለት መጻሕፍተ ኪዳን ቀሌሜንጦስና ዲዲስቅልያ መሆናቸው ያስረዳል። የግእዙ ፍትሐነገሥት ከጳውሎስ መልእክታት ቀጥሎ መጽሐፈ ቀሌሜንጦስን ያስቀምጣል።

በ1990 ዓ.ም የታተመው የፍትሐ ነገሥት ነጠላ ትርጉም ብቻ ቀሌሜንጦስን አልጠቀሰም ከዚህ በስተቀር ከመጽሐፈ ቀሌሜንጦስ የተወሰዱ ኃይለ ቃላት በመጻሕፍተ ሥርዓት በሙሉ ይገኛሉ። በአውሻህር በዲዲስቅልያ በመጻሕፍተ ሲኖዶስ በሥርዓተ ጽዮን በግፅው በአብጥሊስ ይገኛሉ። ስለዚህ መጽሐፉ ለክርስቲያኖች እጅግ ጠቃሚ በመሆኑ በአማርኛና በግእዝ ተዘጋጅቶ ሊቀርብ ችሏል።

አዘጋጅ ገ/ዮሐንስ ገ/ማርያም

## መግለጫ

ዘመናውያን ጸሐፊዎች የቀሌሚንጦስ ታሪክ በአጥጋቢ ሁኔታ ሊገኝ እንዳልቻለ ይገልጻሉ። በፊሊጲስዩስ 4÷3 የተመዘገበውን መሠረት በማድረግ ዶሚቲያን በተባለው ንጉሥ ቀሌሚንጦስ ሰማዕትነትን እንደተቀበለ ይገመታል። ከይሁዲነት እንደተሰወጠ የሚጠቁም ምንጭ አልተገኘም ስለ ቀሌሚንጦስ ቱርቱልያን፣ ኤራንዮስ፣ ኤጲፋንዮስና ሌሎች የጻፉት ይለያያል። የጴጥሮስ ተከታይነቱ ባልተረጋገጠ መንገድ አስቀምጠውታል። የቀሌሚንጦስ በሰማዕትነት መሞት በአራተኛውና በአምስተኛው ክፍለ ዘመን በተጻፉ አፈታሪኮች ላይ የተመሠረተ ነው። ክሮም ወደ ቆሮንቶስ የተጻፈ መልእክት ስለ ቀሌሚንጦስ በጥቂቱ ፍንጭ ይሰጣል።

ቀሌሚንጦስ ከሰብአ አርድእት ቍጥር እንዳለው ይታመናል። በዘመኑ ቆሮንቶስ፦ ግሪኮች፣ አይሁዶችና ሌሎችም ይኖሩባት ነበር። የንግድ ማእከልም ነበረች፤ ከጳውሎስ መልእክት 1ኛቆ 1÷11-16 ጋር የሚመሳሰል ኃይለቃል የቀሌሚንጦስ መልእክት እንደሆነ በጥቂቱ ከሚገመተው መልእክት ውስጥ አለ። የመልእክቱ ፍሬነገር የቆሮንቶስ ክርስቲያኖች በመለያየታቸው የተጻፈ ነው /ምንጭ ኒው ካቶሊክ ኢንሳይክሎፒድያ ቮሊዩም 3/።

በዜና ሐዋርያት /ገድለ ሐዋርያት/ ስለቀሌሚንጦስ የሚከተለውን ታሪክ እናገኛለን ቀሌሚንጦስ በቅዱስ ጴጥሮስ ትምህርት ካመኑት የመጀመርያው ነው። ጴጥሮስን ተከትሎ "ታቅራ" ወደ ምትባለው አገር ሄደና ከመርከብ እንዲወርዱ በማዕበል ምክንያት ልጇ ጠፍቶባት የምታለቅስ ሴትን አይቶ ቅዱስ ጴጥሮስ "ጠፋ" የተባው ልጅ አብሮት ያለው ቀሌሚንጦስ እንደሆነ በመረዳት ከልጇ ጋር እንዳገናኛት ይገልጻል። ስለቀሌሚንጦስ ከማዕበሉ መዳን ታሪክ አልተገለፀም።

ከእናቱ ጋር ከተገናኙ በኋላ እናትየዋ ቀሌሚንጦስና ወንድሙ ወደሮም ተመልሰው በነበረበት ጊዜ ሁለቱ ልጆች የተመረዘ ውኃን በመጠጣት ለሞት ተጋልጠው እንደነበር ያትታል። ከዚህ ላይ የቀሌሚንጦስ አባት "ቀውስጦስ" ተብሏል። ቀሌሚንጦስ ጳጳስ ሆነና ስሙ ያልተጠቀሰው ወንድሙ በሱ

/በቀሌሚንጦስ/ ዲቁና እንደተሠጠው ይነግረናል። በዚሁ መጽሐፍ በሁለተኛው ምዕራፍ እንደገና የቀሌሚንጦስን ታሪክ ይዘረዝራል "ጴጥሮስ በደቀመዝሙርነት ቀሌሚንጦስን መረጠው" በሚል መነሻነት ዮሐንስ ፊሊጶስና እንድርያስ ሌሎችም ከሰብአ አርድእት መካከል ከጴጥሮስ ጋር እያሉ ቀሌሚንጦስ እናቱ ጠፍታበት እያለቀሰ እንዳገኙት ይመዘግባል እንደመጽሐፉ አገላለፅ፤ ቀሌሚንጦስ እያለቀሰ የተገኘበት ቦታ ወደብ ነበር። እናቱን ከማጣቱ ሌላ በሮማውያን ቋንቋ የሚያናግረው ማጣቱም ሌላው ችግሩ ነበር። እነ ጴጥሮስ በሮማውያን ቋንቋ እናገሩትና ባለበትም ከጴጥሮስ ተምሮ በዮናናውያን ቋንቋ ብዙ መጻሕፍትን መፃፉ ይህ ፅሑፍ ያስረዳል።

መጽሐፈ ቀሌሚንጦስ በቅዱስ ጴጥሮስ እየተነገረው ቀሌሚንጦስ እንደፃፈው ይናገራል። ከጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ የተነገረውን ከዓለም ፍጥረት ጀምሮ እስከዕለተ ምፅአት ያለውን ምሥጢር በዚሁ መፅሐፍ ተገልጿል። ቍጥሩም ከሰማንያ አንዱ መፃሕፍት ነው /በኢትዮጵያ ቤተክርስቲያን/። ብዙዎች የትምህርተ መለኮት ምሁራን ቀሌሚንጦስ ከወንጌላዊ ዮሐንስና ከሐዋርያው ጳውሎስ የቤተ ክርስቲያንን አደራነት መቀበሉን ይመሠክራሉ። የዚሁ መፅሐፍ ዋናው መንፈስም ከነሱ አባባል የራቀ አይደለም።

ዲዲስቅልያ /ዐንቀፅ 42 ቍ.5 የመጀመርያ የሮ ም ጳጳስ በ ጳውሎስ የተሾመ ኢሌንዮስ ሲሆን ከሱ ቀጥሎ በጴጥሮስ የተሾመ ቀሌሚንጦስ ነው ይላል። መጽሐፈ ሲኖዶስ በውስጡ ካሉት ሰባሁለት ዐንቀጾች ውስጥ አምሳሁለቱ ከሐዋርያት በቀሌሚንጠስ በኵል የተለለፉ እንደሆኑ ያስረዳል። በሁለቱ መጻሕፍተ ሲኖዶስ፣ በዲዲስቅልያ፣ በገድለ ሐዋርያትና በሌሎች መፃሕፍተ ሥርዓት የቀሌሚንጦስ ሥራ በብዛት ተዘርዝሯል። አብጥሊስ የተባለው የሐዋርያት መጽሐፍም በቀሌሚንጦስ መነገሩን የሐዋርያት የተባለው መጽሐፍ ያስረዳል።

<u>ማውጫ</u>

1. በስመአብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ ፩ አምላክ ይቤ ቅዱስ ቀሌሚንጦስ እምድሕረዕርገቱ ለእግዚእነ ወአምላክነ ወመድሐኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ ውስተሰማይ። ተፈልጡ አርድእት እስከአፅናፈዓለም ከመይስብኩ ዜና ወንጌል ቅዱስ፤

2. ይሚጥዎሙ ለሕዝብ ሙስተአሚን ወአእምሮ ወያጥምቅዎሙ በቅድስት ጥምቀት ዘሐዲስ ልደት።

3. ወበእንተዝንቱ ፈቀዱ ሐዋርያት ይንስሱ ሎሙ አርድእተ ዘየሐውሩ ምስሌሆሙ ውስተበሐውርት ወእምዝ ነሥአኒ ሊተ ስምዖን ጴጥሮስ ወረሰየኒ ረድአዚአሁ እስመአመንኩ ቦቱ በዘፈነዎ ወጠየቀ ከመውእቱ ርእሰሙ ለሐዋርያት።

4. ወበእንተቃል ዘይቤ እግዚእነ ወመድሐኒነ ኢየሱስክርስቶስ በወንጌል ቅዱስ አንተ ኵኵሕ ወዲበዛቲ ኰኵሕ አሐንፃ ለቤተክርስቲያን ወዓናቅፀሲኦል ኢይክልዋ ወኢይሔይልዋ ወእሁበከ መራሑተመንግሥተ ሰማያት።

5. ወእምድሕረጕንዱይ መዋዕል ነሥአ ፪ አሐወ ወረሰዮሙ አርድእተዚአሁ ወእምዝ ሶበነበርኩ ምስሌሁ ፳ዓመተ ነሥአኒ ወአብፅሐኒ ኀበብሔረ አቡየ ወእምየ እንተስማ መጥሮጵያ ወከሠተ ሊተ ምሥጢራተ ዘመህሮ እግዚእነ

# መጽሐፈ ቀሌሚንጦስ

1. በአብ፣ በወልድ በመንፈስ ቅዱስ ስም አንድ አምላክ ቅዱስ ቀሌሚንጦስ እንዲህ አለ "ከጌታችንና መድሐኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ዕርገት በኋላ የቅዱስ ወንጌልን ዜና ይሰብኩ ዘንድ ተማሪዎች ወደ ዓለም ዳርቻ ሁሉ ተበተኑ።

2. አርድእት ወደዓለም ዳርቻሁሉ ሊበተኑ የቻሉት ሕዝቦችን ወደእምነትና ዕውቀት ለመመለስና ዳግም ልደትን የምታሠጠውን ጥምቀት እንዲያጠምቁዋቸው ነው።

3. ከዚህ በተነሳ ሐዋርያት ከያንዳንዳቸው ጋር አብረው የሚሄዱትን ፈለጉ ከዚህ ጊዜ ስምዖን የተባለው ጴጥሮስ ከሱ ጋር ወሰደኝ የሱ ተማሪ እንድሆንም አደረገኝ እኔ በሱ ትምህርት እሱን በላከው አምላክ አምኛለሁና የሐዋርያት አለቃ መሆኑንም ተረድቻለሁና።

4. ጌታችን መድሐኒታችን ኢየሱስክርስቶስ በቅዱስ ወንጌል "አንተ አለት ነህ" በዚች አለት ላይ ቤተክርስቲያኔን እሠራታለሁ የሲኦል በሮችም አያይሉባትም የመንግሥተሰማያትን ቁልፎች ላንተ እሰጣለሁ" ያለውንም አስታወስኩ።

5. ከጥቂት ጊዜ በኋላ ሁለት ሌሎች ወንድሞችን አስከተለ ተማሪዎቹንም አደረጋቸው። እኔ ከሱ ጋር ሃያ ዓመት ከኖርኩ በኋላ ወደናትና አባት አገሬ ወሰደኝ እቺ አገር "መጥሮጵያ" ትባላለች ጌታችን መድሐኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በደብረዘይት

ኢየሱስ ክርስቶስ በደብረዘይት።

6. ወውእተ ጊዜ ነበሩ ሐዋርያት ወኵሎሙ መሐይምናን ውስተ ዓቢይ ምንዳቤ ወስደት እምኀበዕልዋን ወከሐድያን አይሁድ። እስመአይሁድ ነበሩ እንዘይቀትሉ ኵሎ መሃይምናነ ዘነበሩ።

7. ወእምዝ ሖረ ጴጥሮስ ወቦአውስተአሐቲ ሀገር ወእንዚ ምስሌሁ ወበህየ ረከበነ ዓቢይ ምንዳቤ እምተጋእዞትሙ ለአይሁድ እኩያን ወተዋሥኡቶሙ በእንተልደታ ለማርያም ቅድስት እስመይቤሉ በእንቲሃ ከመኢኮነት እምትዘምደ ይሁዳ ከመያብጥሉ ምፅአቶ ለእግዚእነ ወመድሐኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ ውስተዓለም፣

8. እስመእሙንቱ ነበሩ እንዘይሁቡ ብዙሐ ንዋየ ሕልያነ ለሰብአፅርዕ ወለሰብአሮሜ ከመያርእዩዎሙ በእንተጥፍአተ መሐይምናን ወይክልእዎሙ ለሐዋርያት አንብቦኦሪት ወከመኢያእምሩ ቀዳሚ ፍጥረተ ዓለም።

9. ወሰበርኢኩ ዘንተ ኵሎ ሕማመ ወምንዳቤ ዘመፅአ ላእሌየ እምኀበአይሁድ ከሐድያን ሐሰስኩ እምኀበመምሕርየ ጴጥሮስ ወተስእልክዎ ከመያለብወኒ ወይንግረኒ ዘከመኮነ ቀደሚ ፍጥረተ ዓለም።

10. እስመውእቱ አእመረ ምሥጢራተ ኵሎ እምኀበእግዚእነ ኢየሱስክርስቶስ እንዘአእምር በነገረፅርዕ ወዘመፃሕፍቲሆሙ

ያስተማረውንም ምሥጢር ገለፀልኝ (አብራራልኝ)

6. በዚህ ወቅት ሐዋርያትና ሌሎች አማንያን በከባድ መከራ ላይ ነበሩ መከራውን ያደረሱባቸው ከሐዲዎች አይሁድ ናቸው። ከሐዲዎቹ አይሁዶች ኢየሱስ ክርስቶስን ያመነ ሁሉ እያደኑ በመግደል ላይ ነበሩ።

7. ከዚህ ጀምሮ ጴጥሮስ እኔን አስከትሎ ሄደና ወደአንዲት አገር ደረሰ። ከዚሁ ከሄድንበት አገርም ለኔና ለጴጥሮስ ችግር ገጠመን ችግሩ ከከሐዲዎቹ አይሁድ የመነጨ ነበር ቅድስት ድንግል ማርያም ከይሁዳ ትውልድ የላትም እያሉ በመከራከር ችግር ፈጠሩብን እንዲህ ማለታቸው የጌታችን መድሐኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ወደዚህ ዓለም መምጣት ለመካድ ነው።

8. እነዚህ ከሐዲዎች አይሁድ በመጀመርያ የዓለምን አፈጣጠር እንዳያውቁ ሐዋርያት ኦሪትን እንዳያነቡ ይከለክሉዋቸው ዘንድ እንዲሁም በክርስቶስ ያመኑትን ያጠፉላቸው ዘንድ ለግሪክና ለሮም ሰዎች ብዙ ገንዘብን በመስጠት ላይ ነበሩ።

9. ይህን በኔላይና በጴጥሮስ ላይ የደረሰውን መከራና ችግር ባየሁ ጊዜ (ከከሐዲዎች አይሁድ ዘንድ) ዓለም ከመጀመርያው አንስቶ እንዴት እንደተፈጠረች ያስረዳኝ ዘንድ መምህሬን ጴጥሮስ ጠየቅሁት።

10. ቅዱስ ጴጥሮስ ከጌታችን መድሐኒታችን ኢየሰስ ክርስቶስ ምሥጢርን ሁሉ አውቆ ነበርና እኔም የዕርዓውያንን ጥበብና

ዘሀሉ ምሥጢራቲሆሙ ወጥበባቲሆሙ

11. ወነገርክዎ ለመምህርየ ኵሉ ዘመፅአ ላእሌየ ቀመ ወቅንዓተ በእንተዘፀልኡኒ ወተዓገሉኒ አይሁድ በእንተማርያም ቅድስት እስመአልብየ አእምሮ በኦሪት ወበነቢያት ወብዙሐ ተሥእሉኒ በእንተፍጥረቱ ለአዳም አቡነ።

12. ወፈድፋደ ይፀርፉ ላእለማርያም ንግሥት ወቅድስት ወኢረከቡ ምክንያተ በዘአእምር እክዮሙ ወርኩስ ቃሎሙ።

13. ወነገርክዎ ዘንተ ኵሎ ለመምህርየ ወተከዘ ፈድፋደ ወቦአ ላእሌሁ ቅንአት ወይቤለኒ አነ እከሥት ለከ ኦ ወልድየ ኵሎ ዘተሥእልከኒ ወአሌብወከ እምቀዳሚ ፍጥረተዓለም ወእጤይቀከ በእንተማርያም ቅድስት እሙ ለብርሃን ከመይእቲ ጥዩቀ ዘእንበለአስትቶ እምዘመደይሁዳ ወልደያዕቆብ።

14. ወአዲ እዜንወከ ዘከመወድቀ ሠይጣን እምሰማይ ለቡኬ ኦ ወልድየ ቀሌሚንጦስ ከመእግዚአብሔር ውእቱ ቀዳሚ ወእምቅድመቀዳሚ ሕልው ዘአልቦቱ ጥንት ወኢተፍፃሜት ልዑል ውእቱ መልዕልተልዑላን ሕሊና ዘኢይትአወቅ ወኢ በልባዊ ዘአልቦ ታሕት ወኢላእል ኢ ውሳጤ ወኢ አፍኣ።

15. ዘውእቱ ቀዳማዊ ብሉየመዋዕል ወዘመን ውእቱ

መጻሕፍቶቻቸውን ተምሬ ነበርና።

11. በኔ ላይ ቂምና በቀል አድሮብኝ ነበር ምክንያቱም ስለቅድስት ድንግል ማርያምና ስለአባታችን አዳም አፈጣጠር ሲጠይቁኝ ስለኦሪትና ስለነቢያት የማውቀው ነገር ስላልነበረኝ መልስ ለመሥጠት አልቻልኩም ነበርና ተቸግሬ ነበር።

12. ከሁሉ በበለጠ በማርያም ንግሥትና ቅድስት ላይ ስድብን ያሰማሉ ነገርግን እኔ በማውቀው ክፋታቸውና የረከሰ ቃላቸው ለዚሁ ምንም ምክንያትን አላገኙም ።

13. ይህንን ሁሉ ለመምሬ ነገርኩት እሱም በጣም አዘነ መንፈሳዊ ቅንአትም አደረበት እንዲህም አለኝ "ልጄ ሆይ የጠየቅኸኝን ሁሉ ዘርዝሬ አስረዳሀለሁ አለም ከተፈጠረ ጀምሮ እንስቼ እገልፅላሃለሁ የብርሃን ክርስቶስ እናት ስለሆነችውም ቅድስት ማርያም እነግርሃለሁ እሷ ያለጥርጥር ከያዕቆብ ልጅ ይሁዳ ናት።

14. ሠይጣን ከሰማይ እንዴት እንደወደቀም እነግራሃለሁ ልጄ ቀሌሚንጦስ ሆይ ልብ ብለህ ተከተለኝ ከሁሉም በፊት እግዚአብሔር ይቀድማል መጀመርያ የለውም መጨረሻም የለውም ልእልናው ከሁሉ በላይ ነው በህሊና ሊደረስበት አይቻልም ላይና ታች የለውም ውስጥና ውጭም የለውም።

15. እሱ ከሁሉ የቀደመ ሁኖ ዘለዓለማዊ ነው። አይለይም

ኢይትሌለይ ወኢይዜነው መልእልተኩሉ ውእቱ ወሕልው በስነመለኮቱ መልእልተፍጥ ፍጥረቱ ወእምታ ሕተፍጥረቱ ሥነ ፈጠረ ኀራሃነ ዘብሩህ ዘኢይረክቦ ፅልመት፡፡

16. የሐድር ውስተብርሃናት ዘኢይሬእዩዎ ዓፅይንት ወህልው እምቅድመኩሉ ፍጥረት ገባሬ ኩሉ ወፈጣሬኩሉ ዘሥብሐቲሁ እምኅቤሁ ፈጣሬኩሉ ዘይሴብሕዎ ከመይትዓውቅ ዕበየግርማሁ ወፅንዓሐይሉ ገባሬ ሰማይ ወምድር፡፡

17. ወናሁ እነግረከ ኦ ወልድየ ቀሌሚንጦስ ከመእግዚአብሔር ልዑል እምቅድመኩሉ ፈጠረ መላእክቲሁ በአሠርቱ ትዝምድ ወረሰዮሙ ይሰብሕዎ በሰናይ ዜማ ወማሕሌት በበመዓርጊሆሙ ወዘየዓቢ እምኔሆሙ ይቀርብ ኀበ መንበሩ ለእግዚአብሔር ልዑል፡፡

18. ዘመደ ሳጥናኤል ውእቱ ቀዳሚ እምኵሎሙ መላእክት ዘየዓርጉ ስብሐተ ለእግዚአብሔር ዘእንበለዓርምሞ ወበቀዳሚ እለተእሁድ ዘውእቱ ርእሰመዋዕል ወእለታት ወበኵረ መዋዕል ቦቱ ፈጠረ እግዚአብሔር ሰማየ ሰማያት ወምድረ ወትዝምደ መላእክት ልዑላን፡፡

19. ዝ ውእቱ ዘመደሳጥናኤል መላእክት ወሊቃነመላእክት ኃይላት ወሥልጣናት፣ መናብርት ወአጋእዝት ላእካን

አይነገርምም እሱ ከሁሉ በላይ ነውና በመለኮትነቱም ያለ ነው ከፍጥረቱ ጋር ሁኖ ከሁሉ በላይ ነው፡፡ ከፍጥረቱ በታችም ይገኛል ብርሃንን ፈጠረ እሱም ብርሃን ነው ጨለማ የማያገኘው ብርሃን ነው፡፡

16. በብርሃናት ውስጥ ይኖራል ዓይኖች ሊመለከቱት አይችሉም ከሁሉ አስቀድሞ ያለ ነው ሁሉንም የፈጠረ እሱ ነው ምሥጋናው ከባህርዩ ይወጣል ሁሉን የፈጠረና የሚመስገን እሱ ነው የግርማው መጠን አይታወቅም የሐያልነቱንም ፅናት አይታወቅም ሰማይንና ምድርን ፈጥሯል፡፡

17. ቀሌሚንጦስ ልጄ ሆይ ልዑል እግዚአብሔር ከሁሉ አስቀድሞ መላእክትን በአሥር ክፍል ከፍሎ ፈጠራቸው በመልካም ዜማና ማሕሌትም ያመስግኑት ዘንድ አደረገ የሚያመሠግኑትም በየመዓርጋቸው በመቆም ነው ከመላእክት ሁሉ ትልቅ የሆነው ወደእግዚአብሔር መንበር ይቀርባል፡፡

18. የሳጥናኤል ክፍል የሆነው ነው ከሁላቸው መላእክት የሚቀድመው እነዚህ መላእክት ያለማቋረጥ ለእግዚአብሔር ምሥጋና ያቀርቡ ነበር፡፡ የዕለታት መጀመርያ በሆነው እለተ እሁድ የሰማዮች ሰማይና ምድርን እግዚአብሔር ፈጠረ፡፡ ከፍተኛውን ሥፍራ የያዙት መላእክትም በዚሁ ዕለት ተፈጠሩ፡፡

19. ይህም የሣጥናኤል ወገን ነው መላእክት የመላእክት ዓለቆች ኃይላት መናብርት ሥልጣናት አጋእዝት የሚላላኩ ሱራፌልና

ሱራፌል ወኪሩቤል ፀዳል ወብርሃን መዓልት ወሌሊት፣ ነፋሳት ወማያት:: ወፈጺሞ ዘንተ ኵሉ በቀዳሚት ዕለተ እሁድ ቅድስት በቃሉ ቅዱስ፣

20. ወበእለት እንተፈጠረ እግዚአብሔር ዘንተ ኵሉ ፀለለ መንፈስ ቅዱስ ላእለማያት::

21. በቀዳሚት ዕለት ፈጠረ እግዚአብሔር ሰማየ ታሕቲተ ዘይሬእዮ ዘስሙ ፋሌክ ወበእንተዝ ይትዓወቅ ከመኵሎሙ ሰማያት ይትመሰልዎ ለሰማይ ፋሌክ ዘይሬእዮ ሰብእ ከሡተ:: ወውእቱ ሰማይ ፍሉጥ እምልዑላን ሰማያት እስመመልዕልተሰማይ ዘስሙ ፋሌክ ካልእ ሰማይ መልዕልተውእቱ ሰማይ ካልእ ዘስሙ ድርቂቆን::

22. ወመልእልተውእቱ ሰማይ ነደእሳት ወመልእልተ እሳት ካልእ ሰማይ ወኵሎሙ ሰማያት ምሉአነብርሃን ወፀዳል ዘኢይክሉ አዕይንተሰብእ ነፅሮቶ ወርእዮቶ"

23. ወበእለተሰኑይ ፈለጠ እግዚአብሔር ልዑል ማእከለማያት ዘውስተምድር ወከነ ዕርገቱ ለማይ በዛቲ እለት ከመፀፋቅ ደመና።

24. ወእለተርፉ ማያት ይነብሩ ውስተነፋሳት ለዝሉፉ ወኢያንቀለቅሉ ለፌ ወለፌ።

25. ወበሳልስት እለት አዘዘሙ እግዚአብሔር ለማያት ኪሩቤል ፀዳል ብርሃን መዓልት፣ ሌሊት ነፋሶች ውሆች እነዚህ ሁሉ በቅደምተከተል ተፈጠሩ እግዚአብሔር ይህንን ፈፅሞ በተቀደሰው ቃሉ በተቀደሰቿ እሁድ አስተካከለ::

20. እግዚአብሔር ይህን ሁሉ በፈጠረበት ዕለት መንፈስቅዱስ በውሆች ላይ ሰፍፎ ነበር::

21. በመጀመርያው ዕለት እግዚአብሔር ፋሌክ የሚባለውን ሰማይ ፈጠረ እሱም ዝቅተኛው ክፍል ነው በዚሁም ሰማዮች ሁሉ ይህንን እንደሚመስሉ ይታወቃሉ:: ይህንን ፋሌክ የሚባለውም ሰው ያየዋል:: ይህ ሰማይ ከከፍተኞች ሰማዮች ተለይቶ ዝቅ ያለ ነው ምክንያቱም ፋሌክ ከተባለው ሰማይ ከፍ ያለ ሌላ ሰማይ ያለ ሲሆን ከሱ የቀጠለም ሌላ ሰማይ አለ ስሙ ድርቲቆን ይባላል::

22. ከዚሁ ሰማይ በላይ ነደእሳት አለ ከእሳቱ በላይ ደግሞ ሰማይ አለ ሰማዮች ሁሉ በብርሃን የተሞሉ ናቸው ይህንን ብርሃን የሰውዓይን ሊያየውና ሊመለከተው በምንም ዓይነት አይችልም::

23. እግዚአብሔር ሰኞ እለት በምድር ላይ ባሉ ውሆች መካከልና በሰማይ በላይ ውሆች መካከል ልዩነትን ፈጠረ:: እርስበርሱ እንደተጫጫነ ደመናም ሆነ::

24. የቀሩት ውሆች በነፋሶች መካከል ይኖራሉ ወድያና ወዲህ በማለትም ለመንቀሳቀስ አይችሉም (አይንቀሳቀሱም)::

25. በሦስተኛው ቀን እግዚአብሔር ከሰማይ በታች የነበሩትን

እለይነብሩ ታሕተሰማይ ዘስሙ ፋሌክ ከመይትጋብኡ ውስተ ፩መካን ወያስተርኢ የብስ ወኮነ ከማሁ።

26. ወእምዝ አስተርአየ የብስ እንዘፀብር ውእቱ መሬት ወማይ ቱሱሕ ማይኒ ሀለወ ውስቴታ እምታህቴሃ ነፋስ የዓርግ እምውስተከርሳ ለምድር ወይነፍሕ በዓቅም ወቦቱ የዓርግ ወየ ሐዩ ኩሉ ፍጥረት።

27. ምድርሰ ተፈጥረት በአምሳለ ሰፍነግ እንተትነብር መልእልተ ማይ። ወበዛተ አዘዘ እግዚአብሔር ታውፅእ ሣዕረ ወሐመልማለ ወዕፀወ ዘርዓ ወፌውሰ ወባእዳነሂ።

28. ወበራብዕ ዕለት ፈጠረ እግዚአብሔር ፀሐየ ወወርሐ ወከዋክብተ ከመይኩን ዋዕየፀሐይ ዲበምድር ወያይብሳ ለምድር ወለፅቡር ወያፅንዕ መሬታ።

29. ወበሐምስ ዕለት አዘዞሙ እግዚአብሔር ለማያት ያውፅኡ ትዝሞደዓሣት ዘዘዚአሆሙ ሕብሮሙ ወአዲ ፈጠረ እግዚአብሔር ዘይሠርር ውስተነፋሳት ወአናብርተ ዓበይተ ዘዕፁብ ራእዮሙ።

30. ወበሳድስ ዕለት ፈጠረ እግዚአብሔር እምድር ኵሎ አራዊተ ወእንስሳ ወዕዒያተ ወአዲፈጠሮ እግዚአብሔር ለአቡነ አዳም በዛቲ ዕለት እመሬት ወፈጠራ ለሄዋን እምዐፅመገቦሁ።

31. ወበሳብዕት እለት ፈፂም አዕረፈ እምኩሉ ግብሩ ወሰመያ

ውሆች እሱም ፋሌክ የተባለው ወዳንድ ቦታ እንዲሰበሰቡ አዘዛቸው የብስም ይታይ ዘንድ አዘዘ እሱም ታየ።

26. ውሃው ጨርሶ ሳይለይ የብሱ ጭቃ ሁኖ ታየ መሬትና ውኃ ተደባልቀው ይታዩ ነበር ውሃው ከየብስ ውስጥ ሆነ ነፋስ ደግሞ ከምድር ውስጥ ይወጣ ነበር። በቀስታም ይነፍሳል በዚሁም ሕይወት ያለው ፍጥረት ሁሉ ይኖራል።

27. ምድር ከውሃ ላይ እንደምትኖር የሰፍነግ አምሳያ ሁና ተፈጠረች። በዚችም ምድር ላይ ሣርና ልምላሜ እንጨትም ሌሎችም ይበቅሉ ዘንድ እግዚአብሔር አዘዘ።

28. እግዚአብሔር በአራተኛው ቀን ፀሐይን ጨረቃን ፈጠረ የፀሐይም ዋዕይ ምድርን ከጭቃነትዋ ያደርቃት ዘንድ አደረገ የምድርንም መሬት ያፀናል።

29. በአምስተኛው ቀን ውሆች የዓሣዎችን ዓይነት ያወጡ ዘንድ እግዚአብሔር ውሆችን አዘዛቸው ውሆችም የተለያየ መልክ ያላቸውን ዓሦች አወጡ ከነፋስ በላይ የሚበሩትንም ፈጠረ አስደናቂ መልክ ያላቸውንም ትላልቅ ነብሮች ፈጠረ።

30. እግዚአብሔር በስድስተኛው ቀን ከምድር አራዊትን ሁሉና እንስሳት እንዲሁም ትሎች ፈጠረ። እንዲሁም አባታችን አዳምን በዚችው ዕለት ከአፈር ፈጠረው ሄዋንንም ከጐድኑ አጥንት ፈጠራት።

31. በሰባተኛው ቀን እግዚአብሔር ሥራውን ፈፅሞ ዓረፈ

ሰንበተ ወዘፈጠሮ እግዚአብሔር ለአቡነ አዳም በ፫ቱ ሰዓት በዕለተ ዓርብ በሳድሳይ ዕለት እስመበይእቲ ዕለት ቦአ ቅንዓት ወትዕቢት ላእላሠይጣን።

32. ወአውረዶ እግዚአብሔር ለሠይጣን ዲበምድር እምቅድመይፍጥሮ እግዚአብሔር ለአቡነ አዳም ኮነ አርምሞ ላእለኲሉ ኃይለሰማያት።

33. ወይቤሎሙ እግዚአብሔር አብ ለወልድ ወለመንፈስቅዱስ ንዑ ንግበር ሰብአ በአርአያነ ወበአምሳሊነ ወሶበሰምዑ መላእክት ዘንተ ቃለ እምነበእግዚአብሔር ልዑል መፅአ ላእሌሆሙ ዓቢይ ፍርሐት ወድንጋፄ።

34. ወተበሀሉ በበይናቲሆሙ ሞንትላእለዝ ዓቢይ መንክር ዘንበሣዑ ሠእ፩ ይትክሀለነ አርአያሁ ወአምሳሊሁ ለአምላክነ ወፈጣሪነ ወእምዝ ርእዩ ኲሎሙ መላእክት የማነእግዚአብሔር ናሁ ተሰፍሐት ውስተኲሉ ምድር ወኮነ ኲሉ ዓለም ውስተዕራሁ።

35. ወእምዝ ነሥአ እምኲሉ ምድር ንሥቲተ ሐመደ ወእምኲሎሙ ማያት ነጠብጣበማይ ወእምነነፋሳት ንሥቲተ ወእምዋዕየእሳት ንሥቲተ ወኮነ ኲሎሙ ውስተዕራሁ።

36. ወፈጠሮ ለአቡነአዳም እምእላንቱ ፬ ድኩማን ዘአልቦሙ ሐይል ከመይትአዘዙ ሎቱ ኲሉ ፍጥረት መሬትሰ

ሰባተኛይቱንም ቀን ሰንበት ብሎ ሰየማት አዳምን በዕለተ ዓርብ በሦስት ሰዓት ነው የፈጠረው። ከላይ እንደተገለፀው በስድስተኛው ቀን አዳም ተፈጠረ። በዚችውም ዕለት ትዕቢትና ቅንዓት በሠይጣን ላይ አደረ።

32. እግዚአብሔር አባታችን አዳምን ከመፍጠሩ አስቀድሞ ሠይጣንን ወደምድር አወረደው። በዚህ ጊዜ የሰማያት ኀይሎች በሙሉ ለተወሰነ ጊዜ ፀጥ አሉ።

33. እግዚአብሔር አብ ለወልድና ለመንፈስቅዱስ በአርአያችንና በአምሳላችን ሰውን እንፍጠር አላቸው መላእክት ይህን ከልዑል እግዚአብሔር በሰሙ ጊዜ ከላያቸው ላይ ከባድ ፍርሐትና ድንጋጤ አደረባቸው።

34. በየራሳቸውም "ይህ ትልቅ አስደናቂ ተአምር የምንሰማው ምንድር ነው የፈጣሪያችንንና የአምላካችንን አርአያና አምሣልንስ ማየት እንዴት ይቻለናል" ተባባሉ ከዚህ ጊዜ ጀምሮ የእግዚአብሔር ቀኝ በምድር ሁሉ ተዘረጋች ዓለም በመላ በእግዚአብሔር መዳፍ ላይ ሁና ለመላእክት ሁሉ ታየቻቸው።

35. እግዚአብሔር ከምድር ትንሽ አፈርን ከመላ ምድር ውሆችም ጥቂት ጠብታን ከነፋሶችም ጥቂት ነፋስን ከዋዕየእሳትም ጥቂቷን አጠራቅሞ በመዳፉ ማህል ሰበሰባቸው ያዛቸውም።

36. እግዚአብሔር አባታችን አዳምን ከነዚያ አራቱ ደካማዎች ፈጠረው አራቱ ኀይል የሌላቸው ናቸው ይህንን ያደረገው

ከመይትአዘዙ ሎቱላእለኩሉ ፍጥረተሰብእ ማይኒ ከመይትአዘዙ ኩሉ ዘይትሐወስ ውስተማይ ወነፋስኒ ከመይትክሐል ዘያስተናፍስ ወእሳት ከመይፅናዕ በዋዕይ ወይርከብ ሐይለ ዘይረድኦ፡፡

37. ወበእንተዝ ፈጠሮ እግዚአብሔር ልዑል ለአቡነአዳም በእዴሁ ቅድስት በአርአያዚአሁ ወበአምሳሊሁ ከመይትወከፍ ጥበበ ወነቢበ ወአእምሮኩሉ ተሐውሶ፡፡

38. ወሶበርእዩ መላእክት ክብረ ወስብሐተ ዓቢየ ዘኮነ ላእለአዳም ፈርሁ እምዕበየግርማሁ ዘከለሎ ወበርሐ ላለገፁ ብርሃነመለኮት ወዘይፈደፍድ ብርሃኑ እምብርሐነፀሐይ ወይበርህ ሥጋሁ ከመኮከበፅባሕ፡፡

39. ወሶበተፈፀመ ፍጥረቱ ለአዳም ወቆመ ውስተኩሉ ምድር ወአርትአ እገሪሁ ዲበጎልጎታ ወሰፍሐ የማኖውስተመካነ ነበተተከለ ዕፀመስቀሉ ለእግዚእነ ወመድሐኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ፡፡

40. ወእምዝ አልበሶ እግዚአብሔር ለአቡነ አዳም ልብሰመንግሥት ወአክሊለሰብሐት ወዕበየ ግርማ ወክብር ዲበርእሱ ወአስተቀፀሎ አክሊለመንግሥት ወበህየረሰዮ ንጉሠ ወካህነ ወነቢየ ወአንበሮ እግዚአብሔር ዲበመንበረክብር፡፡

ፍጥረት እንዲታዘዝለት ነው መሬት ሰው ሁሉ እንዲታዘዝለት ውሃ፣ በውሃ ውስጥ የሚንቀሳቀሱ ሁሉ እንዲታዘዙለት፣ ነፋስ የሚነፍሰውን ሁሉ ለማሸነት ይቻል ዘንድ እሳት፣ በዋዕይ እንዲጠነክርና የሚረዳውን ሐይል እንዲያገኝ፡፡

37. ስለዚህም እግዚአብሔር ልዑል አባታችን አዳምን በተቀደሰች እጁ በአርአያውና በምሳሌው አድርጎ ፈጠረው ይህም ያደረገበት ምክንያት አዳም ጥበብን፡ ነቢብንና ዕውቀትን ሁሉ እንዲቀበል ነው፡፡

38. በአዳም ላይ ታላቅ ክብርና ታላቅ ምሥጋና ባዩ ጊዜ መላእክት ከግርማው ብዛት የተነሳ ፈሩ የመለኮት ብርሃን በአዳም ፊት ይበራ ነበር የአዳም ፊት ብርሃን ከፀሐይ ይበልጥ ነበር ሥጋውም እንደንጋት ኮከብ ይበራ ነበር፡፡

39. የአዳም አፈጣጠር ከተፈፀመ በኋላ አዳም በምድር ላይ ቆመ፡፡ እግሩንም ወደጎልጎታ አቀና ቀኝ እጁንም ጌታችን ወደተሰቀለበት ጎልጎታ ዘረጋ፡፡

40. ከዚህ ጊዜ ጀምሮ እግዚአብሔር አባታችን አዳምን የምስጋና አክሊልን ልብሰመንግሥትን የግርማ ከፍተኛነትን አለበሰው በራሱ ላይም የመንግሥትን አክሊል አቀዳጀው፡፡ በዚህ ጊዜ ንጉሥነትንና ነቢይነትን ሠጠው በክብር መንበር ላይም አስቀመጠው፡፡

41. ወተጋብኡ ኵሎሙ አራዊት ወእንሥሣ ወአዕዋፍ ወኵሉ ዘፈጠረ እግዚአብሔር ወቆሙ ቅድሜሁ ወአድነኑ አርእስተሆሙ ወሰገዱ ለአዳም።

42. ወሰመዮሙ ለኵሎሙ በበአስማተሆሙ ወተአዘዙ ሎቱ ኵሉ ፍጥረት ወዓቀቡ ቃሎ።

43. ወእምዝ ሰምዑ መላእክት ቃለእግዚአብሔር ልዑል እንዘይብል ኦ አዳም ናሁ ረሰይኩከ ንጉሠ ወካህነ ነቢየ ወመስፍነ ወመኰንነ ለኵሉ ፍጥረት ዘገበርኩ ለከ ይስምዑ ኵሉ ፍጥረት ወለቃልከ ይትአዘዙ ወታሕተ እዴከ ይኩኑ ለከ ለባሕቲትከ።

44. ወወሀብኩከ ዘንተ ሥልጣነ ወአባህኩከ ትግበር ዘፈቀድከ።

45. ወሶበሰምዑ መላእክት ዘንተ ቃለ እምኀበእግዚአብሔር ልዑል ፈድፈደ ዓቢይ ግርማሁ ለአዳም በቅድሜሆሙ።

46. ወሶበርእየ ሠይጣን ኃብተፀጋ ዘተውህበ ለአዳም እምኀበእግዚአብሔር ቀንዓ ላእሌሁ እሞይእተ ሰዓት ወአሐዘ የሐሊ በእንቲአሁ ከመይርከብ ምክንያተ ላእሌሁ ከመያስሕቶ ወይትአዘዝ ሎቱ ወያክህዶ ፀጋ እግዚአብሔር እንተነበረት ላእሌሁ።

47. ወውእተ ጊዜ አእተተ እግዚአብሔር እምኔሁ ልብሰስብሐት ወዕበየግርማ ወሰመዮ ስሞ ሠይጣነ

41. አራዊትና እንስሳት ወፎች እግዚአብሔር የፈጠረው ሁሉ ወደአዳም ተሰበሰቡ ከፊቱም ቆመው ራሳቸውን አዘነበሉ። ለአዳምም ሰገዱ።

42. አዳም ለሁሉም በየስሙ ሰየመው ፍጥረት ሁሉም ለአዳም ይታዘዝና ቃሉንም ይጠብቅ ነበር።

43. በዚህ ጊዜ መላእክት "የእግዚአብሔር ቃል" አዳም ሆይ እነሆ ንጉሥ ካህን ነቢይ መስፍን ለፍጥረት ሁሉ ገዢ ስላንተ በፈጠርሁት ሁሉ እንድትሆን አደረግሁ ፍጥረት ሁሉ አንተን ይስሙ ለቃልህም ይታዘዙ ከእጅህ በታችም ይሁኑ ይህንንም ሁሉ ላንተ ብቻ ሠጠሁ"።

44. የፈለግኸውን ታደርግ ዘንድ ይህንን ሥልጣን ሠጠሁህ ሲል ሰሙ።

45. መላእክት ይህንን የልዑል እግዚአብሔር ቃል በሰሙ ጊዜ ትልቁ የአዳም ግርማ በፊታቸው ላይ እጅግ በዛ።

46. ሠይጣን ለአዳም ከእግዚአብሔር የተሠጠውን ኃብተፀጋ ባየ ጊዜ ከዚች ሰዓት ጀምሮ ቅንአት አደረበት በአዳም ላይም ቀናበት እሱንም አስቶ ከእግዚአብሔር የሚያርቅበትን የሱንም ታዛዥ የሚየደርግበትን ተንኰል በማሰብ ከፀጋ እግዚአብሔር አዳምን ለማውጣት ተነሳ።

47. በዚህ ጊዜ እግዚአብሔር በሠይጣን ላይ የነበረውን የምሥጋና ልብስና የግርማ ልዕልና አስወገደ። ሠይጣን ብሎም ሠየመው

እስመተዓበየ ላእለእግዚአብሔር ወኢሆረ በፍናዊሁ ወፈቀደ ክብረ ለርእሱ።

48. ወእንዘሀለወ አዳም ይቀውም ላእለጎልጎታ ናሁ ተጋብኡ ኵሉ ፍጥረት ከመይስምዑ ቃለ እግዚአብሔር ዘይትናገር ምስሌሁ።

49. ወእምዝ መፅአ ደመናብርሃን ወፆሮ ለአዳም ወወሰዶ ውስተገነት ወሖሩ ቅድሜሁ ለአዳም ኵሎሙ ሠራዊተመላእክት ምስለስብሐት ወማሕሌት ወዘምሮ ወጥዑም ዜማ ኪሩቤል ይባርኩ ወሱራፌል ይቄድሱ ቅድሜሁ ወአብፅሕዎ ውስተገነት ወቦአ አዳም ውስተገነት ጊዜ፫ ሰዓት በዕለተ ዓርብ።

## ምዕራፍ ፪ ድቀቱ ለአዳም

1. አዘዞ እግዚአብሔር ለአዳም ኵሉ ትእዛዛተ እምዕፅ ዘውስተገነት ፈድፋደ አዘዞ ከመኢይብላዕ ወእምዝ አምፅአ እግዚአብሔር ላእለአዳም ንዋመ ጥዑመ ወኖመ በውስተገነት።

2. ወነሥአ እግዚአብሔር አሐደ እምዓፅመገቦሁ ለአዳም ዘፀጋም ወፈጠራ እምኔሁ ለሄዋን ወተፈሥሐ ባቲ ወአፍቀራ ፈድፋደ።

3. እሙንቱ እንዘይነብሩ ውስተኤዶም ገነተትፍሥሕት

በእግዚአብሔር ላይ ታብዮአልና በእግዚአብሔር መንገድም አልሄደምና ለራሱም ክብር ወዷልና።

48. አዳም በጎልጎታ ላይ ሳለ ፍጥረታት ሁሉ ወደሱ ተሰበሰቡ የተሰበሰቡበትም ምክንያት ከአዳም ጋር የሚናገረውን የእግዚአብሔር ቃል ለመስማት ነው።

49. ወድያው የብርሃን ደመና መጥቶ አዳምን ተሸከመው ወደገነትም ወሰደው የመላእክት ሠራዊት በዚህ ጊዜ ከአዳም ፊት ለፊት ከምስጋና ጋር ከማሕሌትጋርና ከዝማሬ ጋር በጥዑም ዜማ እግዚአብሔርን እያመሰገኑ ይጓዙ ነበር ኪሩቤል ባንድ በኩል ሲባርኩ ሱራፌልም ይቀድሱ ነበር። አዳም ወደገነት ዓርብ በሦስት ሰዓት ገባ።

## ምዕራፍ ሁለት፡- የአዳም ድቀት (መውደቅ)

1. እግዚአብሔር አዳምን ትእዛዛትን ሁሉ እንዲፈፅም አዘዘው በተለየም በገነት ከምትገኘዋ ዕፅ እንዳይበላ አዘዘው ወድያውም እግዚአብሔር በአዳም ላይ የሚጣፍጥ እንቅልፍን አመጣ እሱም በገነት ተኛ።

2. እግዚአብሔር ከአዳም ግራ ጐድን አንድ አጥንትን ነቀለ ከዚሁም ሄዋንን ፈጠራት አዳም ሄዋንን ባያት ጊዜ (ከእንቅልፍ ነቅቶ) እጅግ ደስተሰኘ በጣምም ወደዳት።

3. እነሱ በገነት ኤዶም ሲኖሩ እግዚአብሔር ክብርንና ግርማን

አልበሶሙ እግዚአብሔር ክብረ መስብሐተ ወግርማ ወተፈስሐ ፊድፋደ በዓቢይ ስብሐት ወግርማ ዘኮነ ላእሌሆሙ ከለሎሙ እግዚአብሔር ለተዋስቦ ወተፈስሑ በእንቲአሆሙ ኩሎሙ መላእክት።

4. ወኮነ በህየ ዓቢይ ፍሥሐ ዘኢኮነ ከማሁ እምቅድመዓለም ወኢይከውን እስከአመይሰማዕ ቃለትፍሥሕት እምኀበእግዚአብሔር።

5. ወነበሩ አዳም ወሄዋን ፫ ሰዓተ ውስተገነት ገነትሰ መልእልት ይእቲ ውስተነፋሳት ወሞድራኒ ሰማያዊት ወትትሌዓል መልዕልተ አድባር ወአውግር ነዋሐት መጠነ ፲ወ ፭ በእመት።

6. ይእቲሰ አምሳለዕፀመስቀል ዘሰፍሐ እዳዊሁ ላእለዕፀሕይወት ወመድሐኒት ዘተተክለ ዲበምድር መስቀል ቅዱስ።

7. ወነበረ ሠይጣን በእከዩ እንዘይቀንዕ በአዳም ወሄዋን በእንተኩሉ ፀጋ ዘተውህቦሙ እምኀበእግዚአብሔር ወእምዝ አመክነየ ወቦአ ላእለአርዌ።

8. ውእቱሰ አርዌ ይሴኒ ላህየ ራእዩ እምኩሎሙ እንስሳ ወአራዊት እስመቀዳሚ ፍጥረቱ በአምሳለ እንስገመል።

9. ወእምዝ ፆሮ ሠይጣን ለአርዌ ወአብፅሖ ውስተገነት በእንተዝ ተሐብአ ሠይጣን ላእለዓርዌ ዘሰናይ ላህየራእዩ

ምሥጋናን አለበሳቸው እነሱም እጅግ እያመሰገኑ ደስ አላቸው ስለተሠጣቸውም ግርማና ትልቅ ምሥጋና በበለጠ ደስ ተሰኙ እግዚአብሔርም ለጋብቻ ወሰነላቸው መላእክት ሁላቸውም ስለአዳምና ሄዋን ደስ አላቸው።

4. ወልድ በግርማ መንግሥቱ ደግሞ ሲመጣ በቀኝ በኩል ከቆሙት ይህን የመሰለ ደስታ እስኪሰማ ድረስ ከዚያ በፊት ተሰምቶ የማያውቅ ደስታ ተሰማ።

5. አዳምና ሔዋን በገነት ለሦስት ሰዓታት ያህል ኖሩ ገነት ከነፋሳት ላይ ሁና መሬትዋ ሰማያዊ ነው ከረጃጅም ተራራዎች በላይ ትገኛለች ከረጃጅም ተራራዎች ገነት የምትገኝበት ከፍታ አሥራአምስት ሜትር ነው።

6. ገነት ክርስቶስ እጆቹን ዘርግቶ የተሠቀለበት ዕፀመስቀል ምሳሌናት ቅዱስ መስቀል በምድር ላይ ተተክሏል።

7. ሠይጣን ግን በክፋቱ ከእግዚአብሔር ለአዳምና ሄዋን በተሠጠው ፀጋ ሁሉ ይቀና ነበር። በአውሬም እያመኻኘ ሠይጣናዊ ተግባሩንና ሠይጣናዊ ምቀኝነቱን ለማካሄድ ተነሳ።

8. ይህ አርዌ ከአውሬዎችና ከእንስሳት ሁሉ የአስተያየቱ ውበት ያማረ ነበር የመጀመርያው አፈጣጠሩ በግመል ግልገል መልክ ነበርና።

9. ከዚያ በኋላ ሠይጣን የምድር አርዌን ተሸክሞ ወሰደው ወደገነትም አስገባው ከዚህ የተነሳም ሠይጣን መልኩ አስደሳች

• እስመ ሶበአእተተ እግዚአብሔር ዕበየክብሩ እምላዕለሠይጣን ኮነ ሕሱመ ራእዩ ፌድፋደ ወኢይክል ወኢመኑሂ እምኩሉ ፍጥረት ይነፅር ሐቤሁ።

10. ወሶበርእየቶ ሄዋን እንዘስውር ውስተአርዌ እምኢተናገረቶ አላ እምጕየት እምኔሁ።

11. ባህቱ አመክነየ ወተሠወረ ውስተዓርዌ ከመዘያመክኒ ወይሜህሮ ለአፍ ነገረ ሰብእ ወያነሥእ መፅሔተ ብርሀተ ወያነብር ማዕከሌሁ ወማእከለአፍ ወይትናገሮ በዘፈቀደ ወይሜህሮ ለዖፍ።

12. ወርእዮ ዖፍ አዎሳለዚአሁ ውስተመፅሔት ኢያስተት ራእዩ ወይመስሉ ከመዘአርአያሁ ወይመፅእ ኀቤሁ ፍጡነ ይትመሀር ነገሮ።

13. ወከማሁ ገብረ ሠይጣን ሶበ ቦአ ላእለአርዌ ሆረ ኀበሄዋን እንተባህቲታ በውስተገነት ወፀውዐ በስማ ወተመይጠት ኀቤሁ ወርእየት አምሳለዚአሃ ወአስሐታ በቃሉ።

14. እስመፍጥረታ ለብእሲት ድኩም ውእቱ ወተአምን ኩሎ ነገረ ዘትሰምዕ።

15. ውእቱሰ በብዝሐእከዩ ዘተናገራ በእንተዕፀ ዘውስተገነት ወነገራ ዘከመጥዑም ፍሬሃ ወይቤላ ሶበትበልዒ እምኔሃ

በሆነው የምድር አርዌ ላይ ተደበቀ። እግዚአብሔር አሳድሮለት የነበረውን የክብር ልዕልና ካስወገደበት ጀምሮ መልኩ እጅግ የከፋና ማንም ወደሱ መመልከት የማይችል ሁኗል።

10. ሄዋን በምድር አርዌ ውስጥ ተሠውሮ ባያናግራት ኑሮ ከሱ ጋር መነጋገር ቀርቶ ደንግድጣና ፈርታ በሸሸች ነበር።

11. • ነገርግን ይህ ሠይጣን በሰው ቋንቋ እየተናገረ ወፍን የሰው ንግግር እንደሚያስተምር ብሩህ የሆነችንም መስታወት አንስቶ በራሱና በወፉ መካከል እንደሚኖር በመምሰልና ወፉን በፈለገው ቋንቋ እንደሚናገረው እንደሚያስተምረው በመምሰል አመካኘ።

12. ወፍ የራሱን ምስል በመስታወት ካየ ያየውን አይጥልም እሱ ራሱ ወደሱ የመጣ ይመስለዋል ከመፅሔቱ የሚታየውንም ምስል ትምህርት ለመማር ወደሱ ይመጣል።

13. እንደዚሁ ሁሉ ሠይጣን ወደአውሬው በገባ ጊዜ ወደሄዋን ሄደ ብቻዋ በገነት ላይ ቁማ ካለችበትም ደረሰና በስሟ ጠራት እሷም ዞር ብላ ተመለከተችው የራሷንም መልክ እንደመስታወት አስመስሎ አሳያት በቃሉም አሳታት።

14. ሴት በተፈጥሮዋ ደካማ ናት የሰማችውን ሁሉ ምንም ሳታመዛዝን ዓሜን ብላ ትቀበላለችና።

15. ሠይጣን በተንኰሉና በክፋቱ ብዛት ያነጋገራት በገነት ስላለችው ዕፅ ነው ዕጿ ጣፋጭ መሆንዋን ከመናገሩ በላይ እሷን ከበላሽ

ትከውኒ አምላከ።

16. ይእቲሰ ፈተወት ትብላዕ እምፍሬዕፅ እስመቀዲሙ አሰምዓት ትእዛዘፈጣሪሃ እግዚአብሔር ልዑል ዘአዘዘ ለአዳም።

17. ወሖረ ጎቤሃ ፍጡነ ወወሃባ እምፍሬዕፅ ይእቲኒ ሖረት ኀአዳም ወወሀበቶ ወትቤሎ ሶበትበልዕ እምኔሁ ትከውን አምላከ።

18. ወውእቱ ሰምዓ ቃለ ወፈቀደ ይኩን አምላከ በከመትቤሎ ወሶበበልዑ እምኔሁ ኮኑ ዕሩቃነ እምፀጋ ዘላእሌሆሙ ይለብሱ ወሶበርእዩ ርእሶሙ ዕሩቃነ እምፀጋ ዘኮነ ላእሌሆሙ ናሁ ተከሥተ ሐፍረቶሙ።

19. ውእተ ጊዜ ገብሩ ሎሙ ሙራሐ እምቈፅለበለስ ዘየዓጥቁ ወከደኑ ሐፍረቶሙ ወኮኑ ውስተ ዓቢይ ሐዘን ፫ ሰዓተ እስመቦአ አዳም ውስተገነት ጊዜ ፫ ሰዓት በዕለተ ዓርብ ወነበረ ውስተፀጋ መንፈሳዊት ወመንግሥት ዘወሀቦሙ እግዚአብሔር ፫ሰዓተ ተዋቀሰሙ ወበ፱ ሰዓት ኮነ ፀዓቶሙ እምውስተገነት ዘእንበለፈቃዶሙ በዓቢይ ሐዘን ወብካይ ወላህ

20. ወእምድሕረለብሱ ቈፅለበለስ አልበሶሙ እግዚአብሔር

አምላክ ትሆኛለሽ አላት።

16. እሷ ልዑል እግዚአብሔር ከዚች ዕፅ እንዳይበላ አዳም መታዘዙን አልሰማችም ነበርና ሠይጣን ጣፋጭነቷን ከነገራት የገነት ዕፅ ፍሬ ለመብላት ወደደች።

17. ሠይጣንም በፍጥነት ሄዶ ከዕፁ ፍሬ ሠጣት እሷም በፍጥነት ወደአዳም ሄደችና ፍሬውን ሠጠችው "ይህን ከበላህ አምላክ ትሆናለህም አለችው"

18. አዳም የሄዋንን ቃል ሰምቶ አምላክ ለመሆን ወደደ እሷ እንዳለችው ሁለቱ ፍሬውን በበሉ ጊዜ ዕራቁታቸው ሆኑ የለበሱት ፀጋእግዚአብሔር ከላያቸው ተገፈፈ በነሱ ላይ ከነበረው ፀጋ እግዚአብሔር ተገፎ ዕራቁታቸው ሲሆኑ ሐፍረታቸው ተገለጠ።

19. በዚህ ጊዜ ከበለስ ቅጠል ቈርጠው ዕርቃናቸውን ለመሸፈን ያህል ቈርጠው ታጠቁ ለከባድ ሐዘን ተጋለጡ ሦስት ሰዓት ሙሉ ያለዕረፍት አለቀሱ አዳም ወደገነት የገባው በእለተ ዓርብ በሦስት ሰዓት ነው ከገባም ጀምሮ በመንፈሳዊ ፀጋና በንጉሥነት ይገኝ ነበር ይህም እግዚአብሔር ለሁለቱ የሠጣቸው ነው። እግዚአብሔር ሁለቱን ብዙ ወቀሳቸው ዘጠኝ ሰዓት ሲሆን በብዙ ልቅሶ በብዙ ዋይታና ጩኸት ሳይወዱ በግድ ከገነት ተባረሩ።

20. የበለስን ቅጠል ለብሰው ከቈዩ በኋላ እግዚአብሔር ቁርበትን

አነዳማእስ ዝ ውእቱ አነዳሥጋነ ዘመልዕልተሥጋነ ልብሰሐዘን ወሕማም።

21 ወሰበወፅኡ አዳም ወሄዋን እምውስተገነት ደቀሱ ወኖሙ በምሥራቀገነት ወነቂሖሙ እምንዋም ተናገሮ እግዚአብሔር ለአዳም ወይቤሎ ኢትሕዝን ናሁ አገብአከ ኀበዘቀዳሚ ንብረትከ እምኀበአውፃእኩከ እምኔሁ በእንተዘዓለውከ ትእዛዝየ።

22. ይእዜኒ ለቡ እንከ ከመበእንተግብረዚአከ ረገምክዋ በእንተ አበሳከ ወሐጢአትከ ወአዲረገምክዎ ለአርዌ ዘአስሐታ ለሔዋን ወወደይኩ እደዊሁ ወእገሪሁ ውስተከርሱ ወረሰይኩ ሲሳዮ ሐመደ።

23 ወለከሰ ኢረገምኩከ ወፈታሕኩ ላእለሄዋን ትኩን ታሕተእገሪከ ለቡ እንከ ከመሰበፈፀምከ ንብረተ ዘፈታሕኩ ላእሌከ ትንበር ውስተምድር ርግምት ናሁ እፌኑ ወልድየ ፍቁርየ ወይወርድ እምሰማይ ዲበምድር ወይለብስ ሥጋ እምድንግል እንተስማ ማርያም እምዘመድከ።

24. አሐርያ ወአሐንፃ ወእሬስያ ውስተዘበናቲሆሙ ትውልድ እምድሕረትውልድ እስከጊዜርደቱ ለወልድ እምሰማይ።

25. ወውእተ ጊዜ ይከውን ቀዳሚተ መድሐኒትከ ወግብአትከ ውስተርስትከ ናሁ እኤዝዞሙ ለውሉድከ ከመሰበሞትከ

አለበሳቸው ይህንንም ቁርበት የሐዘን ልብስ ነው።

21. አዳምና ሄዋን ከገነት ወጥተው ከገነት ወደስተምሥራቅ በኩል ተኙ ከእንቅልፋቸውም ሲነቁ እግዚአብሔር አዳምን ተናገረው እንዲህም አለው "አትዘን እነሆ ትእዛዜን አፍርሰህ ከወጣህበት ገነት መልሼ እንድትገባ አደርጋለሁ"።

22. እንግዲህ ልብ በል በንተ የሥሕተት ሥራ ምድርን ረገምኩዋት ይህም ባንተ በደልና ሐጢአት ምክንያት ነው ዳግመኛም ሄዋንን ስለሳታት እባብን ረገምኩት እጅና እግሩንም ወደሆዱ እንዲገባና ምግቡም አፈር እንዲሆን አደረግሁ።

23. አንተን ግን አልረገምኩህም ሄዋንን ግን ካንተሥር እንድትሆን ፈርጄባታለሁ እንግዲህ አስተውል ባንተ ላይ የፈረድኩትን ፍርድ ስትጨርስ ባንተና በሄዋን ምክንያት ምድር ስለተረገመች በኋላ ልጅንና ወዳጄን እልከዋለሁ እሱም ከሰማይ ወደምድር ይወርዳል ማርያም ተብላ ከምትጠራው ድንግልም ይወለዳል እሷም ያንተ ዘር ናት።

24. እሷንም እገነባትና እመርጣታለሁ ትውልድ አልፎም ትውልድ እየተተካ ወልድ ከሰማይ እስኪወርድ ድረስ ይቈያል።

25. በዛን ጊዜ የድሕነትህ መጀመርያ ይሆናል ወደ ርስትህም ትመለሳለህ አንተ በሞትክ ጊዜ ከርቤና ዓልው በተባሉ የሽቱ

ይፅቀቡ ሥጋከ በከርቤ ወዓልው ወያነብርዎ ውስተመዛግብት እስከአመይወፅኡ ውሉድከ እምደብር ቅዱስ።

26. ወይገብኡ ውስተምድር ርግምት ወአዝዞሙ ለውሉድከ ዘይሄሉ አሜሃ እምውሉዶሙ ይፁሩ ሥጋከ ምስሌሆሙ ወይሰድዎ ውስተመካን ዘእነግሮሙ አነ እስመውእቱ መካን ዘያነብሩ ሥጋከ ውስቴቱ በህየ እገብር መድሐኒተከ ወመድኃኒቶሙ ለኩሎሙ ውሉድከ።

27. እስመውእቱ መካን ዘያነብሩ ሥጋከ ውስቴቱ በህየ እገብር መድኃኒተከ ወመድኃኒቶሙ ለኩሎሙ ውሉድከ ወከሠተ እግዚአብሔር ለአዳም ኩሎ ዘይመፅእ ላእሌሁ ሐዘነ ወምንዳቤ ወሕማመ ወአዘዞ ከመይትዓገሥ በኩለሄ።

28. ወሶበወፅኡ አዳም ወሄዋን እምውስተገነት ረሰየ እግዚአብሔር ምስሌሆሙ መልአከ ዘእሳት ወውስተ እዴሁ ኲናት ዘእሳት።

29. ወሐደሩ አዳም ወሄዋን መልእልተደብር ቅዱስ ዘስሙ መጥርዮን ዘመልእልቴሁ ገነተትፍሥሕት።

30. ወነበሩ ህየ ውስተበዓት መልዕልተ ርእሰ ውእቱ ደብር እንዘደናግል ንፁሐን እሙንቱ።

ዓይነቶች ቀብተው አሥከሬንህን በቤተመዛግብት ያኖሩት ዘንድ ልጆችህን አዛቸዋለሁ ልጆችህ ከደብር ቅዱስ እስኪወጡ ድረስም ከዚያ ትቆያለህ።

26. ወደተረገመች ምድርም ልጆችህ ይሰበሰባሉ ልጆችህንም በቤተመዛግብት ተጠብቆ ከኖረ በኋላ ሥጋህን ከነሱ ጋር ይውሰዱት እኔ ወደማመለክታቸውም ቦታ ይውሰዱት። ያ ቦታ ያንተን ሥጋ ካኖሩበት በኋላ ዘመን ያንተን መድሐኒትና የልጆችህንም መድሐኒት እንዲገለፅበት (እንዲፈፀምበት) አደርጋለሁ።

27. ያ ያንተን ሥጋ የሚያኖሩበት ቦታ ለወደፊት ያንተን ድሕነት የማሳይበት ቦታ ይሆናል በዚሁም ያንተና የልጆችህ ድሕነት ይገለፃል" አለው እግዚአብሔር ለአዳም ለወደፊት በዚች በተረገመች ምድር ሐዘን መከራና በሽታ እንደሚፈራረቁባት ከነገረው በኋላ እንዲታገሥ ነግሮታል።

28. አዳምና ሄዋን ከገነት በወጡ ጊዜ እግዚአብሔር በገነት በር ላይ እሳታዊ መልአክን አቆመ ይህ መልአክ በእጁ ላይ የእሳት ጦር ነበር።

29. አዳምና ሄዋን መጥርዮን ተብሎ ከሚጠቀስና በገነት በታች ከሚገኘው ደብር ቅዱስ ኖሩ።

30. በዚሁ ደብር ላይ ባንድ ዋሻ ውስጥ በንፅሕና ና በድንግልና ሁነው ለመኖር ቻሉ።

31. ወእምዝ ሶበፈቀደ አዳም ምስሌሄዋን ነሥአ እምታሕቴሃ ለገነት ወርቀ ወከርቤ ወዕጣነ ባረከሙ ወቀደሶሙ ውስተይእቲ በዓት እስመረሰየ ሎቱ ቤተፀሎት ወወሀበ ለሄዋን ወርቀ ከርቤ ወዕጣነ ወይቤላ ንሥኢ ዘንተ ኩሉ እምሃለወልደእግዚአብሔር ጊዜ ምፅአቱ ውስተዓለም፡፡

32. ወርቅ ትእምርት ለመንግሥቱ ወዕጣንኒ ለሕላዌመለኮቱ ወከርቤ ለግንዘተሥጋሁ ዘይነሥእ እምኔነ ወይኩን ዝንቱ ስምዓ ማእከሌየ ወማእከሌኪ በነበመድሐኒነ አመይመፅእ ውስተዓለም፡፡

33. ወሰመያ አዳም ለይእቲ በዓተመዛግብት እምድሕረፀአቶሙ ለአዳም ወለሄዋን እምውስተገነት ነበሩ ፲ዓመተ በዓቢይ ሐዘን ወብካይ ወላሀ፡፡

34. ወእምዝ ወረዱ እምደብር ወነበሩ መትሕቴሁ ወበህየ አእመራ አዳም ለሄዋን ወፀንሰት ወበፅሐ ዕለተወሊዶታ ወወለደቶ ለቃየል ወለእህቱ ሉድ፡፡

35. ወዳግመ ፀንሰት ወበፅሐ ዕለተወሊዶታ ወወለደቶ ለአቤል ወለእህቱ አቅሌምያ መንታ

36. ወልሕቁ እሙንቱ ደቂቅ ወአዋልድ ወበፅሑ ለተዋስቦ ወይቤላ አዳም ለሄዋን ናሁ እግዚአብሔር አልሐቆሙ

31. አዳም ከሄዋን ጋር እያለ ከገነት እግርጌ ወርቅን፣ ከርቤንና ዕጣንን ያዘና ቀደሰው ባረከውም በዚች ዋሻ ለራሱ የጸሎት ቦታ አዘጋጅቶ ነበርና ይህንንንም ወርቅ ዕጣንና ከርቤ ለሄዋን ሠጣት እንዲህም አላት "ይህንን ሁሉ ያዥ እጅ መንሻ ነውና አምሃነቱም ወልደእግዚአብሔር ወደዚህ ዓለም ሲመጣ ይሆናል"፡፡

32. ወርቅ የወልደ እግዚአብሔር መንግሥት ምልክት፣ ዕጣን የህላዌመለኮቱ ምልክት ከርቤ ከኛ ለሚለብሰው ክቡር ሥጋው መገነዣ ናቸው፡፡ ይህም ወልደአምላክ እኛን ለማዳን ወደዚህ ዓለም በሚመጣበት ጊዜ በኔና ባንቺ መካከል ምስክር ይሆናል" አለ፡፡

33. አዳም እቺን ዋሻ ቤተመዛግብት ብሎ ሰየማት አዳምና ሄዋን ከገነት ወጥተው አሥር ዓመት በሙሉ በልቅሶ ብዋይታና በታላቅ ሐዘን ነበሩ፡፡

34. አዳምና ሄዋን ከደብር ቅዱስ ወርደው ከሱ በታች ተቀመጡ በዚሁ አዳም ሄዋንን ተገናኛት እሷም ፀነሰች የመውለጃዋ ጊዜም ደረሰ ቃየልንና ሉድንም መንታዎች ወለደች፡፡

35. ዳግመኛም ሄዋን ፀነሰች የመውለጃዋም ጊዜ ደረሰ መንታዎቹን አቤልንና አቅሌምያንም ወለደች፡፡

36. እነዚህ ሁለት ወንዶችና ሁለት ሴቶች የአዳም ልጆች አድገው ለጋብቻ ደረሱ አዳም ይህን ተመልክቶ ሄዋንን እንዲህ

ለውሉድነ ርቱዕ ያውስባ ቃየል ለአቅሌምያ እህቱ ለአቤል ወአቤል ያውስባ ለሉድ እህቱ ለቃየል።

37. ወሐለዩ ከመዝ ወይቤላቃየል ለሄዋን ኦ እምየ ሊተሰ ይደልወኒ ተሀቡኒ እህትየ ዘተወልደት ምስሌየ ትኩነኒ ብእሲትየ ወተሀቡ ለአቤል እህቶ ዘተወልደት ምስሌሁ ትኩኖ ብእሲተ።

38. እስመለሉድ ይሴኒ ላህያ እምነ አቅሌምያ ወትመስል ከመእማ ሄዋን ወሶበ ሰምዓ አዳም ዘንተ ነገረ ተከዘ ወሐዘነ ፈድፋደ ወይቤሎ ለቃየል ኦ ወልድየ ዝንቱ ዘተሐሥስ ውፁእ እምህግ።

39. ወውእተ ጊዜ ፀንዓ ላእለቃየል ቅንዓት ፈድፋደ ወፈቀደ ይቅትል እሁሁ ወእምዝ ይቤሎሙ አዳም ለአቤል ወለቃየል ሕረዩ ዘታቀርቡ እምፍሬምድር ንፁሕ ወመሐስእ እምውሉደአባግዕ።

40. ወዕርጉ መልእልተደብር ቅዱስ ወባኡ ውስተበዓተመዛግብት ወፀልዩ በህየ ቅድመእግዚአብሔር ወአቅርቡ ሎቱ ዘትፀውሩ እምፍሬያት ወእመሐሥዓ አባግዕ ቁርባነ።

41. ወሶበትገብሩ ከመዝ ትነሥኡ ለለአሐዱብእሲተ እምኔክሙ።

እግዚአብሔር እነዚህ ልጆቻችንን አሳደጋቸው ስለዚህ ቃየል የአቤልን እህት አቅሌምያን ያግባት አቤል ደግሞ የቃየልን እህት ሉድን ያግባት" አላት።

37. አዳምና ሄዋን በዚሁ ተስማሙ ቃየል ግን እናቱን ሄዋንን "እናቴ ሄዋን ሆይ ለኔ ሚስት ትሆነኝ ዘንድ ከኔጋር የተወለደችውን ሉድን ልትሠጡኝ ይገባል ለአቤል ደግሞ ከሱ ጋር የተወለደችውን እህቱ አቅሌምያን ሚስት ትሆነው ዘንድ ትሠጡት ይገባል" አላት።

38. ቃየል እንዲህ ሲል የቻለበት ምክንያት የሉድ መልክ እንደናቷ ሄዋን መልከመልካም ስለነበረ ነው አዳም የቃየልን አባባል ሰምቶ እጅግ አዘነ ቃየል ሆይ አንተ ካንተ ጋር የተወለደችውን መንትያህ ልታገባ አይገባም ህግ አይፈቅድምና" አለው።

39. በዚህ ጊዜ በቃየል ላይ ቅንዓት አደረበት ወንድሙን አቤልንም ለመግደል ፈለገ። ወድያው አባታቸው አዳም ለአቤልና ለቃየል "ለእግዚአብሔር መስዋዕትን ታቀርቡ ዘንድ ከምድር ፍሬና ከበግ ግልገሎች መርጣችሁ አቅርቡ" አላቸው።

40. አዳም ንግግሩን በመቀጠል እንዲህ አላቸው "ወደደብር ቅዱስ ውጡ ከዚሁ ወደሚገኘው በዓተመዛግብትንም ግቡ ከዚሁም ሁናችሁ በመጀመርያ ለእግዚአብሔር ጸሎት አድርሱ ወድያውም የተሸከማችሁትን ፍሬና በግ ለቁርባን አቅርቡ።

41. ይህን ከፈፀማችሁ በኋላ የየራሳችሁን ሚስቶች ትወስዳላችሁ።

42. እሙንቱሰ ገብሩ በከመአዘዞሙ አቡሆሙ አዳም ወእንዘየዓርጉ ውስተደብር ቅዱስ ቦአ ሠይጣን ውስተልበቃየል ወረሰዮ የሐሊ ይቅትሎ ለአቤል።

43. እምዝ አቅረቡ ቍርባኖሙ ቅድመ እግዚአብሔር ወተወክፈ እግዚአብሔር መሥዋዕቶ ለአቤል ወመነነ መሥዋዕቶ ለቃየል እስመእግዚአብሔር አእመረ ህሊናሁ ለቃየል ዘከመይፈቅድ ይቅትል እሁሆ።

44. ወርእየ ቃየል ዘተወክፈ እግዚአብሔር መሥዋዕቶ ለአቤል ወመነነ መሥዋዕቶ ተወሰከ ላእሌሁ ቅንዓት ወቁጥዓ ወመዓት።

45. ወእንዘይወርዱ እምደብር ፀንዓ ቃየል ላእለአቤል ወነሥአ እብነ ወዘበጠ ዲበድማሁ ወቀተሎ።

46. ወረገሞ እግዚአብሔር ለቃየል ወረሰየ ትዕምርተ ወኮነ ርኡደ ወድንጉፀ ኵሎመዋዕለሕይወቱ ወአውረዶ እግዚአብሔር እምደብር ቅዱስ ምስለብእሲቱ ኀበምድር ርግምት።

47. ወነበሩ ህየ አዳም ወሄዋን ወሐዘኑ ላእለዓቤል ዓቢየ ኀዘነ ወለሃው ወእምዝ አእመራ አዳም ለሄዋን ወፀንሠት ወወለደቶ ለሴት ብእሲ ዘሰናይ ራእዩ ሐያል ወዕኑዕ ወፍፁም በራእይ ከመእቡሁ አዳም ወአፍቀሮ

42. ሁለቱ ወንድማማች ቃየልና አቤል አባታቸው አዳም እንዳዘዛቸው አዳረጉ ወደደብር ቅዱስ በመውጣት ላይ እያሉም ሠይጣን ወደቃየል ልብ ገባ አቤልን ወንድሙን ለመግደል እንዲነሳሳ አደረገው።

43. ሁለቱ ቃየልና አቤል ቁርባናቸውን በእግዚአብሔር ፊት አቀረቡ እግዚአብሔር ግን የአቤልን መሥዋዕት ተቀበለ የቃየል መሥዋዕትን ግን አልተቀበለም እግዚአብሔር የቃየልን ወንድሙን ለመግደል መነሳሳቱን አውቋልና።

44. ቃየል የሱን መሥዋዕት ሳይቀበል እግዚአብሔር የዓቤልን መስዋዕት መቀበሉን ሲመለከት ቅንዓቱ ዕጥፍ ሆነ ቅንዓቱ ቁጣውና ንዴቱ ተጨመረ።

45. ከደብር ቅዱስ አቤልና ቃየል እየወረዱ እያለ ቃየል በአቤል ላይ ጨከነ በድንጋይም ማህል ራሱን መትቶ ገደለው።

46. እግዚአብሔር ወንድሙን አቤልን በመግደሉ ረገመው በሱ ላይም ልዩ ምልክት አሳደረ በፍርሐት በድንጋጤና በጭንቀት ይኖር ዘንድም አደረገው እሱንና ሚስቱንም ከደብረቅዱስ ወርደው በተረገመች ምድር እንዲኖሩ አደረገ።

47. አዳምና ሄዋን ባሉበት ሁነው በአቤል ሞት ምክንያት አዘኑ አለቀሱም ከዚህም በኋላ አዳም ሄዋንን ተገናኛት እሷም ፀንሳ ሴትን ወለደችው ሴት መልከመልካም ብርቱ፣ ፅኑና መላቁመናው እንዳባቱ አዳም ሆነ እግዚአብሔርም በዚች ምድር

እግዚአብሔር ከመይኩኖሙ አቡሆሙ ለኩሎሙ ሐያላንምድር።

48. ወአውሰባ ለሉድ እስመቀዳሚ ወለዶ ሴት ለሄኖስ ወሄኖስ ወለዶ ለቃይናን ወቃይናን ወለዶ ለመላልኤል።

49. እስመእሉ አበው ተወልዱ በመዋዕለሕይወቱ ለአዳም ወእምዝ ሐይወ አዳም ፱፻ወ፶ ዓመተ እስከአመኮኖ ለመላልኤል ፻፴ወ፰ ዓመት።

50. ወሶበበፅሐ ጊዜዕረፍቱ ለአዳም ፀውዖሙ ለሴት ወለሄኖስ ወለቃይናን ወለመላልኤል ወፀለየ ላእሌሆሙ ወባረኮሙ ወአዘዞ ለሴት ወልዱ ወይቤሎ ስማዕ ኦ ወልድየ ኩሎ ትእዛዘ ዘእኤዝዘከ ወደይ ውስተልብከ።

51. ወሶበበፅሐ ጊዜፍልሰትከ እምዝንቱ ዓለም አዝዞ ለወልድከ ሄኖስ ወሄኖስ የአዝዞ ለቀይናን ወቀይናን ለመላልኤል ከመይዕቀቡ ዛተ ትእዛዘ ወውሉዶሙ እምድኅሬሆሙ።

52. ትውልድ እምድሕረትውልድ ወሕዝብ እምድሕረሕዝብ ወቀዳሚ ዘእኤዝዘከ ሶበሞትኩ ዕቀብ ሥጋየ በዓልው ወከርቤ ወአንብሮ ውስተበዓተመዛግብት መልእልተደብር ቅዱስ እስከአመይወፅኡ እምደብር ቅዱስ ውሉድከ ወአግዋሪከ እምገነተ ትፍሥሕት።

ለሚኖሩ ሐያላን ሁሉ አባታቸው ይሆናቸው ዘንድ አደረገው።

48. ሴት ከቃየል ጋር ተወልዳ ለአቤል ተሠጥታ የነበረችውን ሉድን አገባት ከዚያበኋላ ሄኖስን ወለደው ሄኖስ ቃይናንን፣ ቃይናን መለልኤልን ወለዱ።

49. እነዚህ አበው አዳም በሕይወት እያለ ነው የተወለዱት ከዚያ በኋላ አዳም ዘጠኝ መቶ አምሳ ዓመት ኖረ አዳም እያለ መላልኤል የመቶ ሠላሳ ስምንት ዓመት ሰው ሁኖ ነበር።

50. አዳም የመሞቻው ጊዜ ሲደርስ ሴትን ሄኖስን ቃይናንንና መላልኤልን ወደሱ ጠራቸው በነሱ ላይም ጸለየ ባረካቸውም ልጁ ሴትንም ልጄ ሴት ሆይ የማዝህና የምነግርህን ነገር ሁሉ ልብ ብለህ ስማ ወደልብህም አስገባው።

51. ከዚህ ዓለም የምትለይበት ጊዜ ሲደርስ ልጅህ ሄኖስን እንዲህ ብለህ እዘዘው “አንተ ቃይናንን እዘዝ ቃይናንም መላልኤልን ይዘዘው በዚሁም መንገድ ቅደምተከተልን ይዘው ልጆችህ ይዘዙ ይህችንም ትእዛዝ ይጠብቁ።

52. ትውልድ አልፎ ሌላ ትውልድ እየተተካ ሕዝብም አልፎ ሌላ ሕዝብ ሲተካ እኔ በምትኩ ጊዜ የኔን ሥጋ በተለያዩ መልካም ሽቶ ዓይነቶች ቀብተህ ጠብቀው በበዓተ መዛግብት (በደብረቅዱስ)ም አኑረው ጎረቤቶችህና ልጆችህ ከደብር ቅዱስ ወጥተው ወደገነት እስኪገቡ ድረስም ከዚያ ይኑር።

53. ወይፁሩ ሥጋከ ምስሌሆሙ ወያንብርዎ ለሥጋከ በዓቢይ ዑቃቤ ውስተማእከለምድር እስመበውስተ ምድር በውእቱ መካን ይከውን አሜሃ ይእተ አሚረ መድሐኒትከ ወመድሐኒቶሙ ለኩሎሙ ውሉድከ ወውሉድየ ወኵንኖሙ ለሕዝብከ በርቱዕ ወበፈሪሃ እግዚአብሔር።

54. አርሕቅ ነፍሰከ ወውሉድከ እምውሉደ ቃየል ቀታሊ ወአዲ ለቡ ሰዓታተ ዘመዓልት ወዘሌሊት ዘከመ መፍትው ታስተበቁዕ ኀበእግዚአብሔር ወትሥእል ኀቤሁ እስመመሐረኒ እግዚእየ ዘንተ ኵሎ ወነገረኒ አስማቲሆሙ ለኩሎሙ አራዊት ወእንስሳ ወአዕዋፈ ሰማይ።

55. ወእምዝ አለበወኒ እግዚአብሔር ኍልቀሰዓታት ዘመዓልት ወነገረኒ ዘከመይሴብሕዎ መላእክት ለእግዚአብሔር።

56. ለቡ እንከ ወልድየ በቀዳሚ ሰዓተ መዓልት የዓርግ ጸሎቶሙ ለውሉድየ መሃይምናን ኀበእግዚአብሔር ወበካልእ ሰዓት ይከውን ጸሎቶሙ ለመላእክት ወአስተብቍእቶሙ ወበሣልስ ዕለት ይሴብሕዎ አዕዋፈ ሰማይ።

57. በራብዕ ዕለት ያመልክዎ መንፈሳውያን ወበሐምስ ዕለት

53. ሥጋህንም ይሸከሙ ከነሱ ጋርም ወስደው ያስቀምጡት ትልቅ አጠባበቅንም ያድርጉለት በምድር ላይ በዚችም ምድር ያን ጊዜ ያንተ ድሕነትና የኔንም ሆነ የኔልጆችም ድሕነትን የሚያገኙበት ጊዜ ያን ጊዜ ይሆናልና። ከዚህም በማያያዝ ሕዝቦችህን በመልካም አመራር ምራቸው እግዚአብሔርንም እንዲፈሩ አስተምራቸው።

54. ራስህንና ልጆችህን ከነፍሰ ገዳዩ አቤል ቤተሰብ አርቅ የቀኑንና የሌሊትንም ሰዓቶች አስተውል ስእታቶቹ እያፈራረቅህ እግዚአብሔርን የምታመሰግንና እሱንም የምትለምን እንድትሆን። ይህንን ሁሉ አምላኬ አስተምሮኛል የእንስሳትንና አራዊትንም ሁላቸው ስም ነግሮኛለ የሰማይ ወፎችንም ስም ነግሮኛል።

55. ከዚህም በላይ እግዚአብሔር የቀን ሰዓቶችን ቁጥር ነገረኝ ከዚሁም ላይ መላእክት እሱን እንዴት እንደሚያመሰግኑት ገለፀልኝ።

56. ልጀ ሆይ ማስተዋል ካንተ አይለይ፣ በመጀመርያው የልጆቼ ጸሎት ወደአምላክ ይቀርባል በሁለተኛው ሰዓት የመላእክት ጸሎትና ምልጃቸው ወደእግዚአብሔር ይቀርባል በሦስተኛው ቀን ወፎች አምላክን ያመሰግናሉ።

57. በአራተኛው ዕለት መንፈሳውያን እግዚአብሔርን ያመሰግኑታል

ይሴብሕዎ ኵሉ እንስሳ ወአራዊት ወበሳድስ ዕለት ይከውን ስእለቶሙ ለኪሩቤል ወበሳብዕ ዕለት ይበውኡ መላእክት ኀበእግዚአብሔር ወይወፅኡ እምኀቤሁ እስመበዛቲ ሰዓት የዓርጉ ስእለቶሙ ኀበእግዚአብሔር ለኵሎሙ ሕያዋን።

58. በሰመንቱ ሰዓት ይሴብሕዎ ሰማያውያን ብሩሃን ወበ፱ ሰዓት ይትቀነዩ ኀበእግዚአብሔር ወይቀውሙ ቅድመመንበሩ ለእግዚአብሔር ልዑል ወበ፲ ሰዓት ይፄልል መንፈስ ላእለማያት ወይጕይዩ ኵሎሙ አጋንንት ወይሴስሉ እምነማያት።

59. ወሶበኢፀለለ መንፈስቅዱስ ላእለማያት በዛቲ ሰዓት ኵሉ ዕለተ እምኢክህለ ወኢመኑሂ ሰትዮተማይ ወእምአማሰነ ሥጋሁ እምኀበአጋንንት እኩያን።

60. ወሶበነሥአ ካህን ማየ በዛቲ ሰዓት ወቶስሐ ምስሌሁ ዘይተ ቅዱሰ ወቀብዓ ቦቱ ድውያነ ወእለቦሙ መናፍስት ርኵሳን ይትፌወሱ እምደዌሆሙ።

61. ወበ፲ወ፩ ሰዓት ይከውን ፍስሐሆሙ ለፃድቃን ወበ፲ወ፪ ሰዓት ይትዌከፍ እግዚአብሔር ልዑል ጸሎቶሙ ወሥእለቶሙ ለኵሎሙ ውሉደሰብእ።

62. በቀዳሚት ሰዓተሌሊት የአኵትዎ አጋንንት ለእግዚአብሔር

ያመልኩታልም በአምስተኛው ቀን እንስሳና አራዊት ሁሉ ያመሰግኑታል በስድስተኛው ዕለት የኪሩቤል ምስጋና ይቀርባል በሰባተኛው ቀን መላእክት ወደእግዚአብሔር ይገባሉ። ከሱም ዘንድ ይወጣሉ በዚችው ዕለት የሕያዋንን ሁሉ ልመናቸው ያቀርባሉና።

58. በስምንት ሰዓት ብሩሃን ሰማያውያን እግዚአብሔርን ያመሰግናሉ በዘጠኝ ሰዓት መላእክት ለእግዚአብሔር ይገዛሉ በልዑል እግዚአብሔር መንበር ፊትም ይቆማሉ በአሥር ሰዓት መንፈስቅዱስ በውሆች ላይ ያንዣብባል በዚህ ጊዜ አጋንንት ከውሃው ወጥተው ይባረራሉ ከውሃም ይወገዳሉ።

59. መንፈስቅዱስ በውሆች ላይ በያንዣብብ ኑሮ በዚችው ሰዓት ሁልጊዜ ማንም ሰው ውሃን ለመጠጣት ባልቻለም ነበር። አጋንንትም የሰውን ሥጋዊ ሕይወት እያሳመሙ ሰውን ሁሉ በጨረሱ ነበር።

60. በዚችው ሰዓት ካህን የተቀደሰውን ዘይት በውሃ ጨምሮ በአጋንንት የተያዙና በሌላም ደዌ የተያዙትን በሽተኞች ቢቀባበት ካደረባቸው ደዌ ይፈወሳሉ።

61. በአሥራ አንድ ሰዓት (ከቀኑ) የጻድቃን ደስታ ይበዛል በአሥራሁለት ሰዓት ልዑል እግዚአብሔር የሁላቸውን የሰው ልጆች ጸሎትና ልመና ይቀበላል።

62. በምሽቱ አንድ ሰዓት አጋንንት ልዑል እግዚአብሔርን

ልውል ወአልቦሙ እከይ ላእለሰብእ ወኢመኑሂ እኩየ እስከይፈፅሙ ቅኔሆሙ።

63. በዳግም ሰዓተሌሊት ይሴብሕዎ ዓሣት ወኩሉ ዘይትሐወስ ውስተማይ አራዊት ወአናብርት። ወበሳልስት ሰዓት ትሴብሆ እሳት ለእግዚአብሔር እስከመትሕተታሕቲት ወበዛቲ ሰዓት አይክል መኑሂ ተናግሮ።

64. ወበራብዕት ሰዓተሌሊት ይሴብሕዎ ሱራፌል በሐምስ ሰዓተ ሌሊት ይሴብሕዎ ማያት ዘመልዕተሰማያት።

65. ነበርኩ እንዘእሰምዮሙ ለመላእክት በዛቲ ሰዓት እንዘይበርሑ ከመድምፀ መንኩራኩር ዓበይት ወአዲ ይፀርሑ መዋግዳት በቃለስብሐት ለኄር እግዚአብሔር።

66. ወበሳድስ ሰዓተሌሊት ይሴብሕዎ ለእግዚአብሔር ደመናት ወብርሃናት ወበረድ ወበሳብዕሰዓተ ሌሊት ብዙሕ ሱባዔ ይከውን በደሐሪ መዋዕል ይትፌፀም ኩሉ ወይበፅሕ ጊዜሁ ወትበልዕ ኩሉ ዘረከብከ ቅድመእግዚአብሔር ወትትቀደስ ምድር ወየሐውር ዳቤሃ እግዚአ አጋ እዝት።

ያመሰግኑታል በዚች ሰዓት ውስጥ ማንኛውንም ሠይጣናዊ ተግባራቸው ያቆማሉ የእግዚአብሔርንም ተገዢነታቸው እስኪወርሱ ድረስ በሰው ላይ አደጋ አያደርሱም።

63. በሁለተኛው ሰዓተሌሊት አሦችና ማንኛውም በውሃ ውስጥ የሚንቀሳቀስ አውሬዎችና ነብሮች እግዚአብሔርን ያመሰግኑታል በሦስተኛው ሰዓተሌሊት እሳት እግዚአብሔርን ታመሰግነዋለች የእሳት ምሥጋና እስከመትሕተታሕቲት ይደርሳል በዚችው ሰዓት ማንም መናገር አይችልም።

64. በአራተኛው ሰዓተሌሊት ሱራፌል እግዚአብሔርን ያመሰግኑታል ባምስተኛው ሰዓተሌሊት ከሰማያት በላይ ያሉ ውሆች እግዚአብሔርን ያመሰግኑታል።

65. ከገነት በነበርኩ ጊዜ መላእክት በዚችው ሰዓት እግዚአብሔርን ሲያመሰግኑት እሰማቸው ነበር ድምፃቸውም እንደትላልቅ መንኩራኩር ይሰማኝ ነበር ሞገዶችም ለደገኛው እግዚአብሔር በከፍተኛ ድምፅ ምስጋና ሲያቀርቡ እሰማ ነበር።

66. ከሌሊቱ በስድስት ሰዓት ደመናዎች ብርሃናትና በረድ እግዚአብሔርን ያመሰግናሉ ከሌሊቱ በሰባት ሰዓት የብዙ ሱባዔ ያርጋል ይፈፀማልም በኋለኛው ዘመን ሁሉ ይፈፀማል ጊዜውም ይደርሳል አንተም ያገኘኸውን ሁሉ ትበላለህ (በእግዚአብሔር ፊት) ምድርም ትቀደሳለች ወደሷም የጌቶች ጌታ እግዚአብሔር ይሄዳል።

67. ወጸሐፈ ሴት በማሕተሙ ዘንተ ትእዛዘ ወበማሕተመአቡሁ
አዳም ወበማሕተመ እሙ ሄዋን ዘነሥአ እምኔሁ እምውስተ
ገነት ውሉዱ ወውሉደውሉዱ እድወአንስት።

68. ወተጋብኡ ወባረኮም አዳም ወጸለየ ላእሌሆሙ አስተብቍአ
ወሰዓለ በእንቲአሆሙ ከመይርከቡ ሣህለ ወዳሕና ወሰላመ።

69. ወሞተ አዳም በ፱፻፴ ዓመት ወተጋብኡ ለግንዘቱ ኲሎሙ
ሠራዊተመላእክት በእንተዕበዩ ለአዳም ቅድመእግዚአብሔር
ወገነዞ ሴት ወልዱ ወአንበሮ ውስተታቦት በምሥራቀገነት።
ኀበነበሩ ቀዳሚ አመያወፅአሙ እግዚአብሔር እምውስተገነት

70. ወሶበሞተ አዳም ፀልሙ ፀሐይ ወወርኀ ሰቡዓ መዋዕለ
ወሰቡዓ ለያልየ ወእምዝ ነሥአ ሴት ወልዱ መፅሐፈ
ትእዛዝ ወአንበራ ውስተ በዓተመዛግብት ምስለቁርባን
ዘነሥአ ምስሌሁ እምውስተ ገነት ዝ ውእቱ ከርቤ ወርቀ
ወዕጣነ ዘነገሮ አቡሁ አዳም ወይቤሎ ናሁ ይገብእ ዝንቱ
ኀበ፫ ነገሥት እምሰብዓሠገል ወይወስድዎ
ለመድሐኔዓለም አመይትወለድ በሀገረ ቤተልሔም።

67. ሴት በራሱ ማሕተም ባባቱ አዳም ማሕተምና በናቱ ሄዋን
ማሕተም ከሱ ጋር የወሰዳቸውን ልጆቹንም የልጅ ልጆቹን ሁሉ
ጻፈ ይህንን ያደረገበት ምክንያት ካባቱ አዳም ስለታዘዘ ነው።

68. እነዚህ የሴት ልጆች በሙሉ በሴት አማካይነት ወደ አዳም
ተሰብስበው አንድም ሳይቀር ቀረቡ አዳምም ስለነሱ ድሕንነት
ስለሰላምና አማላጅነት ብዙ ጸሎት ወደ እግዚአብሔር እየፀለየ
ብዙ ሰዓታትን ካሰለፈ በኋላ ባረካቸው።

69. አዳም በዘጠኝ መቶ አምሳ ዓመቱ ሞተ በመገነዣውም ጊዜ
የመላእክት ሠራዊት በሙሉ ተሰበሰቡ አዳም በእግዚአብሔር
ዘንድ ታላቅ ክብር ተሠጥቶታልና ነገር ግን የገነዘው ልጁ ሴት
ነው። ሴት የአዳምን ሥጋ ከገነት በስተምስራቅ አቅጣጫ
በታቦት ውስጥ አስቀመጠው ይህ ቦታ እግዚአብሔር ከገነት
ባወጣቸው ጊዜ አዳምና ሄዋን የኖሩበት ነው።

70. አዳም በሞተ ጊዜ ፀሐይና ጨረቃ ለሰባት ቀንና ለሰባት ሌሊት
ጨለሙ ያ የጻፈውንም የትእዛዝ መፅሐፍ ሴት በቤተመዛግብት
አስቀመጠው ለቁርባን የተባለውንም ዕቃ ከዚሁ ጋር
አስቀመጠው ለቁርባን የተባለው ዕቃ ሴት ከገነት የወሰደው
ዕጣን፣ ወርቅና ከርቤ ነው። ስለዚህም አዳም ለሴት ይህ
ዕጣን ከርቤና ወርቅ ወደሶስቱ የሰብዓሰገል ነገሥታት እጅ
ይገባል እነሱም ክርስቶስ መድሐኔዓለም በቤተልሔም ሲወለድ
ለእጅ መንሻ ይወስዱታል አለው።

71. ወኮነ ዕረፍቱ ለአዳም ጊዜ ፫ ሰዓት በዕለተ ዓርብ አመሰቡዑ ለሚያዝያ አመረቡዑ ለሠርቀሌሊት ወበዘከመዝ ዕለት አማሕፀነ ነፍሶ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ውስተ ዕደ አቡሁ።

72. ወኮነ ሐዘን ወላህ ላእለውሉደአዳም ወውሉደውሉዱ ፵ መዓልተ ወተፈልጡ አሕዛብ ትዝምደቃየል ወትዝምደ ሴት እምድሕረሞቱ ለአዳም።

73. ወእምዝ ነሥአ ሴት ወልዶ ወውሉደ ውሉዱ ወአንስቲያሆሙ ወዓዕረጎሙ ውስተደብር ቅዱስ ኀበነበረ አዳም ወነበሩ ቃየል ወውሉዱ ወውሉደውሉዱ መትሕተውእቱ ደብር መካነ ኀበቀተሎ ለአቤል።

74. ወኰነነ ሴት ሕዝቦ በፅድቅ ወበንፅሕ ወበቅድስና ዘአእመሮ ነገረ ወዜናሁ ለአዳም ወትእዛዛቲሁ።

## ምዕራፍ ፫ መጽሐፈ ትእዛዘ አዳም

1. ኦ ወልድየ ቀሌሚንጦስ እምሐበሰብአሰገል እለመፅኡ ኀበማርያም እግዝእትነ ጊዜ ልደቱ ልእግዚእነ ኢየሱስክርስቶስ ረከብነ ምስሌሆሙ መጽሐፈዛቲትእዛዝ ዘተፅሕፈ ውስቴታ ዘእከሥት ለከ ወእከ ይእዜ ወናሁ አሌብወከ ኵሎ ዘአእመርኩ ምሥጢራተ ወበእንተ ዘተሰምየ ወልደአዳም ሴት ብሂል።

71. አዳም ዓርብ በሦስት ሰዓት ሚያዝያ ሰባት ቀን በጨረቃ አቈጣጠር አራት ቀን ሞተ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም በተመሳሳይ ሰዓት ነፍሱን ወዳባቱ አደራ ብሏል።

72. በአዳም ልጆችና በልጅ ልጆቹ ትልቅ ሐዘንና ልቅሶ ሆነ አርባ ቀን ሙሉ ሳያቋርጡ አለቀሱ። አዳም ከሞተ ጀምሮ ነገደሴትና ነገደቃየል ለሁለት ተከፈሉ።

73. ሴት ልጆቹን የልጅ ልጆቹንና ሚስቶቻቸውን ወደደብር ቅዱስ አስወጣቸው አዳም ከዚሁ ኑሯልና ቃየልና ልጆቹ እንዲሁም የልጅ ልጆቹ ግን ከደብር ቅዱስ በታች ከሚገኘው ቦታ ውስጥ ይኖሩ ነበር አቤል በዚሁ ነው የተገደለው።

74. ሴት ሕዝቦቹን በቅድስናና በንፅሕና ያስተዳድራቸው ነበር ካባቱ አዳም የተነገረውንም ዜና አስተማራቸው።

## ምዕራፍ ፫ የአዳም የትእዛዝ መፅሐፍ

1. ልጄ ቀሌሚንጦስ ሆይ ጌታችን መድሐኒታችን ኢየሱስክርስቶስ በተወለደ ጊዜ ሰብአሠገል ወደቅድስት ድንግል ማርያም መጥተው ነበር ከነሱ ጋር አብሮ አንድ መፅሐፍ መጥቷል ከዛሬ ጀምሮ ለብዙ ጊዜ የምነግህ ምሥጢር ከዚሁ መፅሐፍ የሠፈረና የተገኘ ነው። የአዳም ልጅ ሴት ስለተባለበትንም ምክንያት እገልፅልሃለሁ።

2. ሴት ብሂል አጥዕየነ እግዚአብሔር እስመነበሩ አዳም ወሔዋን በንፅሕ ወበ ቅድስና ወበእንተዝ ፀገምሙ እግዚአብሔር ዘንተ ክብረ እስመዘየዓቢ እምኲሉ አስማት።

3. ወነበሩ ሴት ወሕዝቡ እምታሕተገነት መልዕልተደብር ቅዱስ እንዘይባርክዎ ወይቄድስዎ ለእግዚአብሔር በዳሕና ወበሰላም ወኢይሄልዩ ወኢምንተኒ ትካዘዝ ዓለም ወአልቦ ካልእ ግብር ዘእንበለስብሐት ወዘምሮ ዘውስተገነት ወሲሰዮሙ እምፍሬዕፀው ዘሀለው መልዕልተ ደብር።

4. እስመፍሬሆሙ ለእሙንቱ ዕፀው ጥዑም ፈድፋደ በእንተዘይመፅእ እምውስተገነት ዔናመዓዛ ሠናይ።

5. ወነበሩ እሉ ሕዝብ በፅድቅ ወበሂሩት ወአልቦ ላእሌሆሙ ቂም ወቅንዓት ወኢ አስተዋድዮ ወኢትዕቢት ወኢይሄልዩ ፅርፈተ ወኢይነብቡ ሐሰተ ወኢይምሕሉ።

6. ወሶበፈቀዱ ምሕረተ ይዔልል መንፈስ ላእለማያት ወታረምም ኲላ ምድር ወኲሉ ዘዲቤሃ ወይነውሙ ማያት ወበዛቲ ሰዓት ይትነሣእ ካህን ወይቶስሕ ዘይተ ቅዱሰ ምስለማይ ወይቀብዕ ቦቱ ዱያነ ወእለኒ አይነውሙ ሴሲተ እምሕማም ይትፌወሱ ወየሐይው እምደዌሆሙ

2. ሴት ማለት እግዚአብሔር ሆይ ጤና ሥጥ ማለት ነው። አዳምና ሄዋን በንፅሕናና በቅድስና ኑረዋል ስለዚህም እግዚአብሔር ከስሞች ሁሉ እጅግ ከፍ ያለውን ክብር [illegible]።

3. ሴትና ሕዝቡ ከገነት በታች ከምትገኘው ደብር ቅዱስ ላይ ነበሩ ከዚህም ሁነው እግዚአብሔርን መቀደስና ማመስገን ብቻ ሥራቸውን አደረጉ የዚህን ዓለም ትካዜ ፈፅሞ አይታ[illegible] ነበር። ከምሥጋና በቀርም ሌላ ሥራ አልነበረውም ምግባቸውም ከደብር ቅዱስ የተተከሉት የዛፍ ፍሬዎች ነበር።

4. የደብር ቅዱስ ዛፎች ፍሬ እጅግ ጣፋጭ ነበር ይህ የሆነበት ምክንያት መልካም መዓዛ ከገነት እየተነሳ ወደነሱ [illegible] ስለነበር ነው።

5. እነዚህ ህዝቦች በፅድቅና በደግነት ብቻ ይኖሩ ነበር ቂም ቅንአት ነገሥሪነት ትዕቢት የስድብን ነገር ማሰብ ፈፅሞ ከነሱ ዘንድ አልነበረም ሐሰትንም መናገርና ማሰብ ፈፅሞ ከያንዳንዳቸው ህሊና ርቆ ነበር።

6. የእግዚአብሔርን ምህረት በፈለጉ ጊዜ መንፈስቅዱስ በውሆች ላይ ያንዣብባል ምድርም በመለዋ ፀጥ ትላለች በሷ ላይ ያለውም ሁሉ እንዲሁ ፀጥ ይላል ውሆችም ይተኛሉ በዚህ ጊዜ ካህን ተነስቶ ቅዱስቅብእን ከውሃ ጋር በማደባለቅ የታመሙትን ቢቀባቸው እንቅልፍ ያጡትንም ቢቀባቸው ከደዌአቸው ይፈወሳሉ

ወይነውሙ፡፡

7. ወበሳምንት ዕለት ታወፅእ ምድር ሣዕረ ወሐመልማለ ወታበቊል ዕፀወ፡፡

8. ወበታሥዕ ሠዓት ይትቀነዩ መላእክት ለእግዚአብሔር ወትበው እፀሎቶሙ ለውሉደሰብእ ቅድመ እግዚአብሔር፡፡

9. ወበአሥር ሰዓት ይትረሐው ዓና ቅፀሰማይ ወይሰምዕ እግዚአብሔር ጸሎቶሙ ለውሉደመሐይምናን ወይትወሀቦሙ ሥዕለቶሙ ዘይስእሉ እምሀበእግዚአብሔር ወበድምፀክነፊሆሙ ለሱራፌል ይነቁ ዶርሆ ውእተ ጊዘ ይሴብሐዎ ለእግዚአብሔር፡፡

10. በ፲ወ፩ ሰዓት ይከውን ፍሥሐ ወሐሴት ዲበምድር እስመፀሐይ ይበውእ ውስተገነት ወይሠርቅ ብርሃኑ ውስተኩሉ አፅናፈ ዓለም ወያበርሕ ላእለፍጥረት፡፡

11. ወበ፲ወ፪ ሰዓት መፍትው ለውሉድየ ይቁሙ ቅድመእግዚአብሔር ወይትቀነዩ እስመበዛቲ ሰዓት ይከውን ንሥቲት ዓርምሞ ላእለኩሎሙ ሰማያውያን፡፡

12. አእምር ዘንተ ኩሉ ወስምዓኒ ነገርየ ወለቡ ከመቃለ እግዚአብሔር ልዑል ይወርድ እምሰማይ ዲበምድር በከመነገረኒ ጊዜ አውፅአኒ እምገነት፡፡

13. እስመውእቱ ይቤለኒ ከመቃሉ ይሰባእ በደሐሪ መዋዕል

እንቅልፍ በማጣት የተቸገሩትም እንቅልፍ አግኝተው ይተኛሉ፡፡

7. በስምንተኛው ዕለት ምድር ሣዕርንና ልምላሜን ታበቅላለች የተለያዩ ዕፀዋትንም ታበቅላለች፡፡

8. በዘጠኝ ሰዓት መላእክት ለእግዚአብሔር ይገዛሉ የሰው ልጆችም ሁሉ ጸሎት ወደልዑል እግዚአብሔር የምትደርሰው በዚሁ ሰዓት ነው፡፡

9. በአሥር ሰዓት የሰማይ በሮች ይከፈታሉ በዚህ ጊዜ የመሐይምናን ሁላቸው ጸሎት ከእግዚአብሔር ዘንድ ይደርሳል ከእግዚአብሔር ዘንድ በንፁሕልብ የለመኑትም ይፈፀምላቸዋል፡፡ የሱራፌል ድምፅም በመስማት በዚሁ ሰዓት ዶሮ ይጮኻል ወድያውም ፍጡራን ሁሉ እግዚአብሔርን ያመሰግኑታል፡፡

10. በአሥራ አንድ ሰዓት ፍፁም ደስታ ይሆናል• (በምድር ላይ) ፀሐይ ወደገነት ይገባልና የፀሐይም ብርሃን በዓለም ሁሉ ወጥቶ ፍጥረት ሁሉ በፀሐይ ብርሃን እንዲደሰት ይሆናል፡፡

11. በአሥራ ሁለት ሰዓት ልጆቼ በፀጥታ ይቆሙ ዘንድ ይገባል የሚቆሙትም ከእግዚአብሔር ፊት ነው ለሱም ይገዙ በዚች ሰዓት ሰማያውያን ሁሉ ለጥቂት ጊዜ ፀጥ ይላሉና፡፡

12. ይህን ሁሉ ስማ ነገሬንም አድምጥ ልብ ብለህም አዳምጥ የእግዚአብሔር ቃል ከሰማይ ወደምድር ይወርዳል ይህንንም እግዚአብሔር አምላኬ ከገነት ባስወጣኝ ጊዜ ነግሮኛል፡፡

13. ሕያው እግዚአብሔር ቃሉ በኋለኛው ዘመን ካንዲት ልጅ

እምወለት ድንግል እንተሰማ ማርየም ወይሠወር ውስቴታ ወይለብስ ሥጋሃ ወይትወለድ በአምሳለሰብእ በዓቢይ ሐይል ወበኪነጥበብ አልቦ ዘየአምሮ ዘእንበሌሁ፡፡

14. ወአዲ ይትከሠት ወያንሶሱ ምስለውሉድየ ዲበምድር ወይልሕቅ በመዋዕል ወበዓመታት ወይገብር ተአምራተ ወመንክራተ ክሡተ ወየሐውር በምድር ወየሐውር ዲበመንበር ዲበ ምድር ሐበባሕር ከመየሐውር ዲበየብስ ወይገብር ከመዝ ወይጌሥፅ ባሕረ ወነፋሳተ ወይትአዘዝዎ ገሐደ ወይዔውዖሙ ለመዋግደባሕር ወያወሥኦሙ ፍጡነ፡፡

15. ወይሬስዮሙ ለዕውራን ይርአዩ ወእለለምፅ ይንፅሑ ወፅሙማን ይስምዑ ወበሃማን ይንብቡ ወያነሥኦሙ ለሙታን ወመፃጉዓን የሐይው ወያረውዖሙ ለሐንካሳን ወይ መይጠሙ ለብዙሐን ውስተአእምሮ እግዚአብሔር፡፡

16. ወይሰድዶሙ ለአጋንንት እመላእለሰብእ

17. ወአዲ ነገረኒ ወይቤለኒ ኢትሕዝንአ አዳም እስመፈቀድከ ወዓለውከ ትእዛዝየ ወናሁ እሬስየከ አኮ ይእዜ አላ ባሕቱ እምድሕረሕዳጥመዋዕል፡፡

18. ወካዕበ ዜነወኒ ወይቤለኒ አነ ውእቱ እግዚአብሔር

ማርያም የምትባል ሰው እንደሚሆን ከሷም እንደሚሠወር የሷንም ሥጋ እንደሚለብስ በሰው አምሳልም እንደሚወለድ ነገሮኛል አወላለዱም ከሱ በቀር ማንም ሊያውቀው አይችልም በረቂቅ ሚስጢር ነው የሚወለደው፡፡

14.ግልፅ ሁኖም በምድር ይመላለሳል ከልጆቼ ጋርም ወዲያ ወዲህ ይላል በምድር ላይም ጥቂት በጥቂት ያድጋል በዓመታትና በቀናትም ዕድገቱ ይቀጥላል፡፡ ግልፅ ተአምራትንና መንክራትንም ያሳያል ከምድር በባሕር ላይ በየብስ እንደሚጓዘው ይጓዛል ነፋሳትንና ባሕርን ይገሥፃል እነሱም በግልፅ ይታዘዙለታል የባሕርንም ሞገዶች ይጠራቸዋል እነሱም ፈጥነው አቤቱ እነሆ በማለት መልስ ይሠጡታል፡፡

15. በዚሁም ዕውሮች ያዩ ዘንድ ለምፃሞች ይነፁ ዘንድ መስማት የተሳናቸው ይሰሙ ዘንድ፣ መናገር ያቃታቸው ይናገሩ ዘንድ ሙታን ይነሱ ዘንድ ሽባዎች ይድኑ ዘንድና መሄድ ያቃታቸው ይሄዱ ዘንድና ብዙዎችንም እግዚአብሔርን ወደማወቅ ይመለሱ ዘንድ ያደርጋል፡፡

16. አጋንንትንም ከሰው እያስወጣ ያባርራቸዋል፡፡

17. ድጋሚም እንዲህ አለኝ አዳም ሆይ አትዘን ፈቅደህ ትእዛዜን አፍርሰሃል ስለዚህ የገባሁልህ ቃልኪዳን አሁኑኑ የሚፈፀም አይደለም ከጥቂት ጊዜ በኋላ ግን ይፈፀማል፡፡

18. ዳግመኛም እግዚአብሔር አናገረኝ እንዲህም አለኝ ከገነት

ዘአውፃእኩከ እመውስተ ገነተተፍሥሕት ውስተምድር እንተታበቁል ሦክ ወአሜከላ ወተሐድር ውስቴታ ወአድሕን ርእሰከ ወዘባነከ ወአርእድ ብረኪከ ወርስአነሥጋከ ያስተርኢ ሲሳየ ለለእለት ተሐሥሥ።
19. እምድሕረሐሙስ መዋዕል ወመንፈቀመዓልት እምሕረከ ወእሰሃለከ በብዝሐሣህልየ ወምረትየ ወእወርድ ውስተቤትከ ወአሐድር ውስተከርስከ በእንቲአከ።

20. አዳም እትወለድ ከመሕፃን በእንቲአከ ኦ አዳም አሐውር ውስተምሥያጥ ወበእንቲአከ እፀውም ፵ ዕለተ ወበእንቲአከ እትዌከፍ ሕማማተወዕትዔገሥ እሰቀል ዲበዕፀመስቀል ወዝንቱ ኩሉ በእንቲአከ።
21. ዘሎቱ ስብሐት ወእኒዝ ወዕበይ ወክብር ወሰጊድ ወዘምሮ ምስለአቡሁ ወመንፈስ ቅዱስ እምይእዜ ወእስከለዓለም ዓሜን።
22. ወአዲ አእምር ኦ ወልድየ ሴት ናሁ ይመፅእ አይኅ ዲበምድር በእንተውሉደ ቃየል ቀታሊ ዘቀተሎ ለእሁሁ በቅንአት በእንተ እህቱ ሉድ ወ በእንተዝ አልቦሙ መሐላ ዘእንበለ ደመአቤል ጻድቅ።
23. በልማደሙ እሙንቱ ሕዝብ የዓርጉ መልእልተደብር ቅዱስ ነዑሰሙ ወዓቢዮሙ እድ ወአንስት ኩሎ አሚረ

እውጥቼ እሾህና አሜከላ በምታበቅል ምድር ያስቀመጥኩህ እኔነኝ በሷም ለተወሰኑ ዓመታት ትኖራለህ ጀርባህንና ራስህን በገዛራሳሕ አድን ጉልበትህም ይንቀጥቀጥ የሥጋህ እርድና ይታያል። የየዕለት ምግብህንም ትፈልጋለህ።
19. ካምስት ቀንና ግማሽቀን በኋላ እምርሃለሁ ይቅርታም አደርግለሃለሁ በይቅርታየ ብዛትና በምሕረቴ ብዛትም ወዳንተ ቤት እወርዳለሁ በወገንህም ከርስ አድራለሁ ይህ ሁሉ ስላንተ ድህነት ይሆናል።
20. አዳም ሆይ ሕፃን ሁኜ ስላንተ እወለዳለሁ አዳም ሆይ ስላንተ በገቢያ ሁሉ እመላለሳለሁ አርባ ዕለትም እፆማለሁ ስላንተ ብዙ መከራን እቀበላለሁ መከራውንም እታገሰዋለሁ በዕንጨት ላይም እሰቀላለሁ ይህ ሁሉ የሚፈፀመው ስላንተ ነው።
21. ምስጋና ዘለዓለማዊነት ልዕልና ክብር ሥግደትና ዘምሮ ለአብ ለወልድ ለመንፈስቅዱስ ይገባል እስከዘለዓለሙ ዓሜን።

22. ሴት ልጄ ሆይ ወንድሙ አቤልን በቅንአት ተነሳስቶ ስለገደለው ቃየል ልጆች በምድር ላይ የጥፋት ውሀ ይመጣል ቃየል ስለእህቱ ሉድ አቤልን ገደለው ስለዚህ ከጻድቁ አቤል ደም በቀር ለቃየል ልጆች ሌላ መሐላ የላቸውም።
23. ሕዝቡ ሁሉ (ደቂቀ ሴት የሆኑ) ወደደብር ቅዱስ ይወጡና ከአዳም ሥጋ እየተባረኩ ይመለሱ ነበር ለመባረክ የሚወጡት

ወይትባረኩ እምሥጋአቡየ አዳም::

24. ወበህየ ያነሥኡ አዕይንቲሆሙ ውስተገነት ወይሰግዱ ቅድሜሁ ለእግዚአብሔር ይሴ ብሕዎ ወይቄድስዎ ወይባርክዎ ወእምዝ ይበውኡ ውስተማሕደሪሆሙ::

25. ወሐይወ ሴት ወልዱ ለአዳም ፱፻ ፲ወ፪ ዓመተ ወእምዝ ሐመ ለመዊት ወተጋብኡ ሄኖስ ወቃይናን ወመላልኤል ያሬድ ወሄኖክ ወአንስቲያሆሙ ወውሉዶሙ::

26. ወፀለየ ላእሌሆሙ ሴት ወባረከሙ ወአስተብቁዓ በእንቲአሆሙ ወይቤሎሙ በደሙ ለአቤል ፃድቅ ኢይረድ እ ሞኤክሙ መኑመ እምዝንቱ ደብር ቅዱስ ወኢይደመር ምስለደቂቀቃየል ቀታሊ እስመአንትሙ ተአምሩ ፀልዓ እንተማእከሌነ ወማእከሎሙ እምአመተቀትለ አቤል ጻድቅ::

27. ወእምዝ ቀርበ ኀቤሁ ሄኖስ ባረኮ ወይቤሎ ኦ ወልድየ ኩንኖሙ ለሕዝብ በፅድቅ ወበርትዕ ወሶበሞትኩ ተቀነይ ቅድመ እግዚአብሔር ለዝሉፉ መቅድመሥጋሁ ለአዳም ቅዱስ::

28. ወአምሐሎ በደመአቤል ከመያሰኒ ላእለሕዝቡ በፅድቅ ወበንፅሕ ወኢያፅርዕ ተቀንዮ ቅድመሥጋሁ ለአቡነዳም ወሞተ ሴት ወኮነ ዕረፍቱ በሰሉስ ዕለት አመ፲ለታሕሣሥ ወገነዞ ሄኖስ ወልዱ በከርቤ ወበዓልው ወአንበሮ

ትልቁ ትንሹ ሴቱ ወንዱ ሁሉም ናቸው::

24. ከዚያም ሁነው ዓይናቸው አንስተው ወደገነት ይመለከታሉ ከእግዚአብሔር ፊትም ይሰግዳሉ ይቀድሱታል ያመሰግኑታል ከዚያ ወደማደርያቸው ይመለሳሉ::

25. ሴት ዘጠኝ መቶ አሥራ ሁለት ዓመት ኖረና ሊሞት ታመመ በዚህ ጊዜ ሄኖስ ቃይናን መላልኤል ያሬድና ሄኖክ ከልጆቻቸው ከልጅ ልጆቻቸው ጋር ወደሴት ቀረቡ::

26. ሴት በነሱ ላይ ጸለየና ባረካቸው ስለነሱም ወደእግዚአብሔር ማለደ እንዲህም አላቸው "በአቤል ጻድቅ ስም አደራ እላችሁ አለሁ ከናንተ ማንም ከደብር ቅዱስ ወርዶ ከነፍሰገዳዩ ቃየል ጋር አይደመር ቃየል አቤልን ከገደለው ጀምሮ በኛና በሱ መካከል ያለውን ጥል እናንተ ታውቃላችሁ"::

27. በዚህ ጊዜ ሄኖስ ወደሴት ቀረበ ሴትም ባረከው እንዲህም አለው በቀና መንፈስና በእውነት ሕዝብሕን ምራቸው በሞትኩም ጊዜ ከተቀደሰው የአዳም ሥጋ ፊት ቁመህ ለእግዚአብሔር ተገዛ"::

28. በጻድቁ አቤል ደምም አማለው በሕዝቡ ዘንድ አመራሩን በንፅሕናና በእውነት ያስተካክል ዘንድ በአዳም ሥጋ ሴትን ለእግዚአብሔር አገልግሎቱን እንዳያቋርጥ ነገረው ሴት ሞተ ዕረፍቱም ታሕሣሥ አሥር ቀን ሆነ ሄኖስ አባቱ ሴትን በክብር

ውስተመዛግብት ምስለሥጋ አዳም።

29. ወነበረ ላህ ላእለሕዝብ ፺ ዕለተ ወእምድሕረሞቱ ለሴት ኮነኖሙ ሄኖስ ለሕዝቡ በፅድቅ ወበርትዕ ወገብረ ላእሌሆሙ ኵሉ ዘአዘዞ አቡሁ።

30. ወሶበኮኖ ለሄኖስ ፲፻ ዓመት ቀተሎ ላሜህ ዕውር ለቃየል ቀታሊ በገዳም በውስተዕፀው ወበውስተመካን ዘይብልዎ ኖልእራጋር እስመላሜህ እንዘየሐውር ውስተገዳም ሰምዓ ቃለ ወኢያእመረ ከመቃየል ውእቱ ወመሰሎ ድምፀ አርዌ።

31. ወእምዝ ነሥአ እብነ ወወገረ ቦቱ ኀበድምፅ ዘይትሐወስ በማእከለዕፀው ወደደቆ ለቃየል ማእከለዓዕይንቲሁ ወቀተሎ ወይቤሎ ለላሜህ ወልዱ ዘይመርሆ ናሁ ዘቀተልካሁ ለአቡነ ቃየል ወጠፍሐ እደዊሁ ላሜህ በእንተ ሐዘኑ ላእለቃየል ወበጥፍሐተ እደዊሁ ለከፎ ለወልዱ ወቀተሎ።

32. ወሶበኮኖ ለሄኖስ ፱፻ወ፳ ዓመተ ሐመ ለመዊት ወተጋብኡ ኀቤሁ ኵሎሙ አሐው ወሀለው ምስሌሁ ያሬድ ወሄኖክ ቃይናን ወመላልኤል ወማቱሳላ ወአንስቲያወሙ ወውሉዶሙ ወፀለየ ላእሌሆሙ ባረከሙ ሰዓለ ወአስተብቁዓ በእንቲአሆሙ።

ገንዘው የተለያዩ መልካም ሽቶችንም አፈሰሰለት ከአዳምጋርም በቤተመዛግብት አስቀመጠው።

29. ሕዝቡ በሴት ሞት ምክንያት አርባቀን አለቀሰ ሴት ከሞተ በኋላ ሄኖስ ሕዝቦቹን በቅንና በእውነት መራቸው አባቱ ሴት የነገረውንም ሁሉ ፈፀመ።

30. ሄኖስ ስምንት መቶ ዓመት ሲሞላው ዓይነሥውሩ ላሜህ ነፍሰገዳዩን ቃየልን በዱር ውስጥ በእንጨቶች ማሕል ገደለው ቃየል የተገደለበት ቦታ ኖልእራጋር ይባላል ዕውሩ ላሜህ ቃየልን ሊገድለው የቻለው የዱር አውሬ ድምፅ መስሎ የቃየል ድምፅ ስለተሰማው በመደንገፅ እንጂ ሆን ብሎ አልገደለውም።

31. ቃየል በእንጨቶቹ ውስጥ ድምፁን ሲያሰማ ዕውሩ ላሜህ ዲንጋይን አንስቶ ድምፅ ወደሰማበት አቅጣጫ ቢወረውረው ቃየልን በሁለት ዓይኖቹ ማህል አሳረፈበትና ሞተ በዚህ ጊዜ ይመራው የነበረው ልጁ ዲንጋይ ወርውረህ የገደልከው አባታችን ቃየልን ነው ቢለው ከሐዘኑ የተነሳ በኃይል እጆቹን አራገበና ሲያራግብ የሚመራውን ልጁ ገደለው።

32. ሄኖስ ዘጠኝ መቶ አምስት ዓመት ሲሞላው ታመመ ሊሞትም ተቃረበ በዚህ ጊዜ ያሬድ ሄኖክ መላልኤል ቃይናንና ማቱሳላ ከልጆቻቸውና ከልጅልጆቻቸው ጋር ወደሄኖስ ተሰበሰቡ ሄኖስም ስለነሱ ጸለየ ባረካቸው ስለነሱም ወደእግዚአብሔር ማለደ።

33. ወአምሐሎሙ በደመአቤል ጻድቅ ከመኢይደመሩ ምስለውሉደቃየል ቀታሊ ወይቤሎሙ ተዘከሩ ሰልዓ እንተማእከሌነ ወእንተ ማእከሎሙ።

34. ወቀርበ ቃይናን ኀበአቡሁ ኄኖስ ውእቱኒ ባረኮ ወይቤሎ ኦ ወልድየ ረአዮሙ ለሕዝብከ ወለዘመድከ ወዕቀቦሙ በከመዓቀብክዎሙ አነ ወፍታሕ ላእሌሆሙ በርትዕ ወአዝዞ ለወልድከ መላልኤል ከመይርአዮሙ በርትዕ ወበንፅሕ ወኢያፅርዕ ተቀንዮ ቅድመሥጋሁ ለአዳም አቡነ ኵሎ መዋዕለሕይወቱ።

35. ወሞተ ሄኖስ በቀዳሚት ሰንበት አመሰብዑ ለወርሐጥቅምት አመኮና ለማቱሳላ ፶ወ፺ዓመት ወገነዞ ለሄኖስ ወልዱ ቃይናን ወአንበርዎ ውስተበዓተመዛግብት ወለሀውዎ ለሄኖስ ፵ ዕለተ።

36. ወእምዝ ኮነኖሙ ወልዱ ቃይናን ለሕዝቡ በፅድቅ ወበረትዕ ወዓቀበ ኵሎ ትእዛዘአቡሁ ወሐይወ ፱፻ወ፲ እመተ ወሶበበፅሐ ዕድሜሁ ወጊዜሁ ባረኮሙ ለውሉዱ ወሞተ በረቡዕ ዕለት አመ፲ወ፫ ለወርሐሰኔ ወገነዞ መላልኤል ወሐይወ መላልኤል በፅድቅ ወበርትዕ ፰፻፺፭ ዓመተ።

37. በሶበበፅሐ ጊዜፀአቱ እምዝንቱ ዓለም አዘዞ ለወልዱ ያሬድ

33. በጻድቁ አቤል ደምም ከነፍሰገዳዩ ቃየል ጋር እንዳይደባለቁ አማላቸው እንዲህም አላቸው በኛና በነፍሰገዳዩ ቃየል ያለውን መለያየት አስቡ አትርሱት።

34. ቃይናን ሊሞት ወደቀረበው አባቱ ሄኖስ ቀረበ ሄኖስም ቃይናንን ባረከው እንዲህም አለው ሕዝብህን ጠብቃቸው ዘመዶችህንም ጠብቅ እኔ እንደጠበቅሁዋቸው ጠብቃቸው በነሱ ላይም ትክክለኛውን ፍርድ ፍረድ መላልኤልንም ልጅህን ካንተ በኋላ ህዝቦቹን በትክክል ይመራቸው ዘንድ እዘዘው መላልኤል በአባታችን አዳም ሥጋ ፊት ለእግዚአብሔር መገዛቱንም እንዳያጓድል አደራ በለው።"

35. ሄኖስ በመጀመርያዋ ሳምንት ጥቅምት ሰባት ቀን ሞተ ሄኖስ ሲሞት ማቱሳላ የአምሳሰባት ዓመት ሰው ነበሮ ቃይናን አባቱ ሄኖስን ገነዘው ከዚያ በመዛግብት ዋሻ ቀበሩት ሄኖስ ከሞተ በኋላ ሕዝቦቹ አርባቀን አልቅሷል።

36. ቃይናን የሄኖስ ልጅ ሕዝቦቹን በእውነትና በቅንነት መራቸው የአባቱንም ሄኖስ ትእዛዝ ሁሉ በጥንቃቄ አከበረ ዘጠኙ መቶ ሃያ ዓመትንም ኖረ የመሞቻ ጊዜው ሲደርስ ልጆቹንና የልጅልጆቹን ባረካቸው ሰኔ አሥራ ሶስት ቀን በዕለተ ረቡዕ ሞተ መለራኤል ልጁም ገነዘው መላልኤል ስምንት መቶ ዘጠና አምስት ዓመት ኖረ።

37. መላልኤል ከዚህ ዓለም የሚለይበት ጊዜ ሲደርስ ከሱ በፊት

በከመአዘዙ አበዊሁ እለእምቅድሜሁ ወሞተ በእለተ እሁድ
አመ፬ለሚያዝያ ወገንዘ ያሬድ ወአንበሮ ውስተመዛግብት
ምስለአበዊሁ ሶበኮና ለያሬድ ፳፻ ዓመተ ተንሥኡ እደው
እምውሉደሴት።

38. ወዓለው ትእዛዘአበዊሆሙ ወሀደጉ መሐላ ድሕሬሆሙ ወአሐዙ ይረዱ በበ፩፩ እምደብር ቅዱስ ወተደመሩ ምስለውሉደቃየል እስመሠይጣን አመክነየ ላእሌሆሙ ለውሉደላሜህ ዕውር።

39. እስመተወልዱ ለላሜህ ፪ውሉድ ስሙ ለ፩ቲዮፊል፣ ወለካልኡ በልቄን ወገብሩ እሙንቱ አውታረመሰንቆ ወአርጋኖን ወእንዚራ ወከበሮ ወተውኔተ።

40. ወሶበሰምዑ ደቂቀሴት እለአስገሮሙ ሠይጣን በድምፀዝንቱ ተውኔት ወጥዑም ዜማሁ ወረዱ እምላእለደብር ቅዱስ ወተደመሩ ምስለደቂቀቃየል እኩያን ዘነበሩ በኩሉ ገቢረእኩይ።

41. ወኮኑ ሥሩሐነ በተውኔት በመብልዕ ወበመስቴ ወበዝሙት ወአንስት ይጉይያ ድሕረወራዙት ወራዙትኒ ይጉይዩ ድሕረአንስት ዕራቆሙ ገሀደ ውስተ ምሥያጣት ከመአእዱገ ገዳም።

42. ወአገበሮሙ ሠይጣን ለውሉደሴት ወደመሮሙ ምስለውሉደቃየል በድምፀማሕሌት ወመሰንቆ ወተውኔት

የነበሩትን አባቶቹ እንዳዘዙት እሱም ያሬድን አዘዘው ቃይናን በዕለተ እሁድ ሚያዝያ ሁለት ቀን ሞተ ያሬድም ገንዘ በመዛግብት ዋሻ አስቀመጠው (ከባቶቻችን ጋር) ለያሬድ አምስት መቶ ዓመት ሲሞላው ከሴት ልጆች ወንዶች ተነሱ።

38. ያባቶቻቸውን ትእዛዝ አፈረሱ ከአዳምና ከሌሎችም አባቶች የተረከቡትን አደራነት ጠሉ አንዳንድ እያሉም ከደብር ቅዱስ በመውጣት ከቃየል ልጆች ጋር ተጨመሩ ሠይጣን በታወረው የላሜህ ልጅ አመካኝቶባቸዋልና።

39. የቃኤል ቤተሰብ የሆነው ዕውሩ ላሜህ ሁለት ዮፊልና በልቄን የሚባሉ ልጆች ነበሩት እነዚህ ልጆች በመሰንቆ በአርጋኖን፣ በእንዚራና በከበሮ የታጀበ ዘፈንን ዘፈኑ።

40. የሴት ልጆች በሠይጣን ተታልለው የቃየል ልጆችን መከተል ጀመሩ በዚሁ በጣፈጠውም የዘፈን ዜማ ተመሠጡ ይህንንም መነሻ አድርገው ከደብር ቅዱስ እየወረዱ ከክፉወች የቃየል ልጆች ጋር ተጨመሩ።

41. የሴት ልጆች በዘፈን ተጠምደው ወደቁ በመብል በመጠጥና በዝሙት ተያዙ ሴቶች ጉልማሳዎችን በመከተል ተሯሯጡ። ወንዶችም እንዳዱር አውሬ ዕራቁታቸው እየሆኑ በየገቢያው ይዘሩ ጀመር።

42. ሠይጣን የሴትን ልጆች አሳስቶ ከቃየል ልጆች ጨመራቸው የኸውም በዘፈን ድምፅ በመሰንቆ በጨዋታና በመዳራት

ዘሰሞው እምኀቤሆሙ ወወረዱ እምደብር ቅዱስ ውስተምድር ርግምት፡፡

43. ወግእዙ እምአግዋሪሁ ለእግዚአብሔር ወመነኑ ክብረ እስመፀገዎሙ እግዚአብሔር ልዑል ይትባረክ ስሙ ዘረሰዮሙ ውሉደ በከመይቤ ዳዊት ነቢይ አንዘ ይብል አማልክት አንትሙ ወደቂቀልዑል ኵልክሙ በእንተዘነበሩ በገቢረትእዛዛቲሁ እምትካት ወሰበአበሱ ይቤ በእንቲአሆሙ አንትሙሰ ከመሰብእ ትመውቱ ወከመመልአሐዱ እመላእክት ትወድቁ፡፡

44. እስመስሕቱ ወአርኰሱ ሥጋሆሙ በአዋልዲሁ ለቃየል፡፡ በሐጢአቶሙ እስመገብሩ ብዙሐ ርኵሰ ወፍትወተ ወአገመኑ ነፍሶሙ፡፡ በእከየፍትወት ወነበሩ እንዘ ይሰክቡ ብእሲ ምስለብእሲት በቅድመኵሉ ወየሐውሩ ፪ እደው ወሰለስቱ ኀበአሐቲ ብእሲት ወይሰክቡ ምስሌሃ ዘእንበለሐፍረት፡፡ ወአርኰሱ ኵላ ምድረ፡፡

45. ወተደመሩ ኵሉ ፍጥረቶሙ ወአልቦዘየአምር ውሉዶ እምውሉደካልኡ ወቀነዮሙ ሠይጣን ፈድፋደ እንዘይትፌስሑ ወይትሐሰዩ ወይትፈግዑ በተውኔት

በማታለል ነው ከደብርቅዱስ ወደተረገመችው ምድር የወረዱት፡፡

43. እግዚአብሔር ባለሟሎቹ አድርጎ አስቀምጦአቸው እያለ የአጋንንትን ፈለግ ተከተሉ የአጋንንት ባለሟሎችም ሆኑ ከሕይወት ሞትን መረጡ ክብርን ናቁ ክብር ይግባውና ልዑል እግዚአብሔር አክብሮአቸው ነበር ልጆቹንም አድርጎአቸው ነበር ነቢዩ ዳዊት ስለነሱ "እኔስ አማልክት ናችሁ የልዑል እግዚአብሔርም ልጆች ናችሁ አለ ይህን ማለቱ የእግዚአብሔርን ትእዛዝ በማክበር የነበሩበትን ለማስታወስ ነው፡፡ ከበደሉ በኋላ ስላለው ጊዜአቸው ሲገልፅ ደግሞ "እናንተስ እንደሰው ትሞታላችሁ ከመላእክት አንዱ እንደወደቀም ትወድቃላችሁ" አለ፡፡

44. እጅግ ተሳሳቱ ሥጋቸውንም አረከሱ በቃየል ልጆች አመንዝሩ ብዙ የረከሰ አድራጎትንም ፈፀሙ እጅግ የረከሰ ተግባርንም ፈፀሙ፡፡ ነፍሳቸውንም ረስተው በኃጢአት ተጠመዱ ሴት ከወንድ ጋር ወንድ ከሴት ጋር እንደእንስሳት ሁነው ተገናኙ ግልፅ የአመንዝራነትን ተግባር ፈፀሙ ሁለት፣ ሦስት ሁነው ባንዲት ሴት ላይ ተገናኙ ምድርንም በመላዋ አረከሱዋት፡፡

45. ማነኛውንም ተፈጥሮአቸው ወደቃየል ልጆች ጨመሩ አንዱ ካንዱ ሲለዩ እስከማይችሉ ድረስ ተደባለቁ ሠይጣን ሙሉ በሙሉ ገዛቸው፡፡ በወደቀና በረከሰው ውድቀታቸው

ልበእከየምግባርሙ ወይሰማዕ ድምፀ ስሐቆሙ ከመንቃወአፍራስ ወእዲ ይሰማዕ ድምፀአውያቶሙ በደብርቅዱስ።

46. ወእምድሕረ ገብኡ እምውሉደሴት ፻ብእሲ እደው ሐያላን ወዕኑዓን ወፈቀዱ ይረዱ እምደብር ቅዱስ ወሰበሰሞዓ ያሬድ በእንቲአሆሙ ኀዘነ ፈድፋደ።

47. ወለአከ ኀቤሆሙ ወመፅኡ ወቆሙ ቅድሜሁ ወይቤሎሙ ኢትግበሩ ከመዝ ወገሠፆሙ ወአምሐሎሙ ወይቤሎሙ በደመአቤል ፃድቅ ከመኢይረዱ እምደብር ቅዱስ ወእዲ ይቤሎሙ ተዘከሩ መሐላ ዘመሐልክሙ ቅድመ።

48. ወመፅአ ሄኖክ ወተናገሮሙ ወይቤሎሙ አእምሩኬ ኦ ውሉደሴት ወእመቦ እምኔክሙ ዘሐደገ ትእዛዘ አበው ወነሰተ መሐላ ወወረደ እምደብር ቅዱስ ኢይገብእ ዳግመ እስከለዓለም።

49. እሙንቱሰ ኢተመይጡ ኀበነገሩ ለያሬድ ወኢሰምዑ ቃሎ ለሄኖክ ወወረዱ እምደብር ቅዱስ ወሶበርእዩ አዋልዲሁ ለቃየል በዘይሴኒ ሥነራእይ እንዘየሐውራ ዕራቆን ዘእንበለሐፍረት ተደመሩ ምስሌሆን ወሐጕሉ ርስቶሙ።

50. ወእምድሕረፈፀሙ ዘንተ ፈቀዱ ይትመየጡ ኀበደብር

የሚያሰሙት ጩኸትና ዋይታቸው እንደባዘራ ፈረስ እስከደብር ቅዱስ ተሰማ።

46. አንድ መቶ ኃይለኞች ከደቂቀ ሴት ውስጥ የሆኑ ከደብር ቅዱስ ሊወርዱ ሲዘጋጁ ያሬድ አይቶና ሰምቶ እጅግ አዘነ ስለድቀታቸውም እጅግ ተከዘ።

47. ያሬድ መልእክተኛን ወደሱ ልኮ አስጠራቸውና እነሱም መጥተው ከፊቱ ቆሙ ይህንን የሠይጣን ሥራ አትሥሩ በማለት ገሠፃቸው በፃድቁ አበል ደምም አስማላቸው ከደብር ቅዱስም እንዳይወርዱ አስቀድማችሁ የገባችሁትን መሐላ አስቡ አላቸውም።

48. ሄኖክም መጣና ተናገራቸው እንዲህም አላቸው "ከናንተ መካከል ያባቶችን መሐላ ጥሶ ከደብር ቅዱስ ለመውጣት ያሰበ ካለ ደግሞ ተመልሶ ወደደብር ቅዱስ እስከዘለዓለሙ አይገባም"

49. እነሱ ግን የያሬድን ምክር ሰምተው ወደኋላ ለማለት አልፈለጉም የሄኖክንም ምክር አልተቀበሉም ከደብር ቅዱስ ወርደው በምድር ላይ ታዩ የቃየል ሴቶች ልጆች ተውበው ዕርቃናቸው በመሆን ሲንቀሳቀሱ አዩዋቸውና ከነሱ ጋር አመነዘሩ ርስታቸውንም አጠፉ።

50. እነዚህ ከቃየል ሴቶች ልጆች ጋር ሥጋቸውን ያረከሱ መቶ

ቅዱስ ወከልኦሙ እብነእሳት ዘይነድድ ከመኢይባኡ ወኢክህሉ ገቢአ ወእምድሕረፈቀዱ ካልአን እምውሉደሴት ይረዱ እምደብር ቅዱስ ኢያእመሩ ዘኮነ እብነእሳት ወረዱ ኀቤሆሙ ወአርኰሱ ሥጋሆሙ በርኩሳን አዋልደቃየል፡፡

51. ወሶበኮና ለያሬድ ፱፻ ዓመተ በፅሐ ፍልሰቱ እምዝንቱ ዓለም ወተጋብኡ ኀቤሁ ሄኖክ ወማቱሳላ ወላሜህ ወኖን ወፀለየ ላእሌሆሙ ወባረኮሙ ወይቤሎሙ አንትሙሰ ኢትረዱ ወኢትደመሩ ምስለ ሕዝበቃየል ውሉድክሙ ወአንስቲያክሙስ ይወርዱ፡፡

52. ወእግዚአብሔር ልዑል ኢየሐድጎሙ ይንበሩ በኀጕል ወበዘዓለው ትእዛዞ ወትእዛዘአበው፡፡ ወእምዝ ይቤሎሙ ለውሉዶሙ ናሁ ትትጋብኡ ውስተምድር ርግምት እንተታበቍል ሦክ ወአሜከላ ወዘወፅአ እምኔክሙ እምዝንቱ ደብር ይንሳእ ምስሌሁ ሥጋሁ ለአዳም ወይንሳእ ሥጋሆሙ ለኩሎሙ አበው፡፡ ወአዲ ይንሣእ ምስሌሁ መፅሐፈ ትእዛዝ ወቁርባነ ከርቤ ዕጣነ ወወርቀ ወያንብሮ ምስለሥጋሁ ለአዳም፡፡

53. ወእምዝ ይቤሎ ለሄኖክ አንተሰ ኦ ወልድየ ኢታዕርዕ ስብሆ ወዘምሮ ቅድመሥጋሁ ለአዳም ወተቀነይ ቅድመ

ደቂቀሴት ደብር ቅዱስ በዲንጋይ እሳት መዘጋቱን ሳያውቁ ሊመለሱ ሞከሩ ግን የእሳቱ ዲንጋይ እንዳይገቡ ከለከላቸው ሌሎች የሴት ልጆችም የወገኖቻቸው መመለሻ አጥተው መቅረትን ሳያውቁ ከደብረቅዱስ እየወጡ ወደተረገመችው ምድር ወርደው ከቃየል የረከሱ ሴቶች ጋር አመነዘሩ፡፡

51. ያሬድ ዘጠኝ መቶ ዓመት ሲሞላው ከዚህ ዓለም የሚለይበት ቀን ደረሰ በዚህ ጊዜ ወደሱ ሄኖክ ማቱሳላ ላሜህና ኖን ተሰበሰቡ ያሬድም በነሱ ላይ ጸለየ እንዲህም አላቸው "እናንተ ከደብርቅዱስ አትውረዱ ከቃየል ልጆች ጋርም አትጨመሩ ልጆቻችሁና ሚስቶቻችሁ ግን ከደብር ቅዱስ እየወጡ ከነሱ ጋር ይጨመራሉ፡፡

52. እግዚአብሔር ልዑል ግን እንዲህ እንዳበዱ ይኖሩ ዘንድ አይተዋቸውም የሱን ትእዛዝና የአበውን ትእዛዝ አፍርሰዋልና ለነሱ ልጆች ደግሞ እንዲህ አላቸው "ከዛሬ ጀምሮ በተረገመችው ምድር ልትሰባሰቡ ነው፡፡ ሁላችሁም ደብርቅዱስን ትታችሁ ስትወርዱ ከናንተ ጋር ያባታችን አዳምን ሥጋና የሌሎችንም አበው ሥጋ ይዛችሁ ውረዱ በተጨማሪም ቁርባንን፣ ወርቅን፣ ዕጣንንና ከርቤንም ይዛችሁ ሂዱና ከአዳም ሥጋ ጋር አኑሩት፡፡"

53. ያሬድ ለሄኖክ እንዲህ ሲል መከረው "ልጄ ሆይ አንተግን በአዳም አባታችን ሥጋ ፊት መዘመርንና ማመስገንን አትተው

እግዚአብሔር በዕድቅ ወበርትዕ በኵሉ መዋዕለሕይወትከ።

54. ወሞተ ያሬድ በዕለተ ዓርብ ጊዜ ፫ ሰዓት አመአሥሩ ወሰኑዩ ለወርሐ ግንቦት አመኮኖ ለማቱሳላ ፱፻፷ወ፫ ዓመት። ገነዞ ሄኖክ ወልዱ ወአንበሮ ውስተባዓተመዛግብት።

55. ወመነኖሙ እግዚአብሔር ለእለተርፉ ደቂቀሴት በእንተዘአፍቀርዋ ለሐጢአት ወእምዝ ተፈልጡ ወኮኑ ፪ተ ሕዝበ ወፈቀዱ ይረዱ እምደብር ቅዱስ ።

56. ወሶበሰምዐ ሄኖክ ወማቱሳላ ወላሜህ ወኖኅ ኀዘኑ በእንቲአሆሙ ፈድፋደ ወሶበፈፀመ ሄኖክ ተቀንዮ ፭ተ ዓመተ ቅድመእግዚአብሔር እምድሕረልደቱ በ፫፻፷ወ፭ ዓመት አለበዎ እግዚአብሔር በኵሉ ወዘከመይነሥኦ ኀቤሁ ወውእተ ጊዜ ፀውዖሙ ሄኖክ ለማተሳላ ወላሜህ ወኖኅ።

57. ወይቤሎሙ ናሁ አእመርኩ አነ ከመእግዚአብሔር ልዑል ይትመዓዖሙ ለእሉ ሕዝብ ወይትፋታሕ ላእሌሆሙ ፍትሐኩነኔ ዘአልቦ ምሕረት አንትሙሰ እለተረፍክሙ አበው ትውልደፃድቃን ቅዱሳን ኢታፅርዑ ተቀንዮ ቅድመእግዚአብሔር ወኩኑ ንፁሐነ ወሄራነ ወአእምሩ ከመአልቦ ዘይትወለድ ድሕሬክሙ ዳግመ በዝንቱ

ከእግዚአብሔር ፊትም ተገገርነትህን በእውነትና በቅንነት ግለፅ በዘመንህ ሁሉ ይህ ይሁን ተግባርህ"።

54. ያሬድ ግንቦት አሥራ ሁለት ቀን በዕለተዓርብ በሦስት ሰዓት ሞተ ያሬድ ሲሞት ማቱሳላ ዘጠኝ መቶ ስድሳ አምስት ዓመት ሁኖት ነበር። ልጁሄኖክ ገንዞ በመዛግብት ዋሻ አኖረው።

55. የቀሩትን የሴት ልጆች እግዚአብሔር ችላ አላቸው ሐጢአትን ወደዋታልና ከዚህም የተነሳ ተለያይተው ሁለት ክፍል ሆኑ ጨርሰውም ከደብርቅዱስ ለመውረድ ወደዱ።

56. ሄኖክ፣ ማቱሳላ፣ላሜህና ኖህ ይህንን ሲሰሙ በጣም ስለነሱ መጕፋት አዘኑ ሄናክ ሦስት መቶ ስድሳአምስት ዓመት ሲሆነውና ከያሬድ ሞት በኋላ አምስት ዓመት ለእግዚአብሔር ተገገርነቱን ካሳየ በኋላ እግዚአብሔር የአስተዋይነትን ልቡና ሠጠው ወደሱ እንደሚወስደውም አስረዳው በዚህ ጊዜ ሄኖክ ማቱሳላን ላሜህንና ኖኅን ጠራቸው።

57. እንዲህም አላቸው "እነሆ ልዑል እግዚአብሔር በነሱ ላይ ቁጣውን እንደሚገልፅ አወቅሁ በነሱ ላይ እጅግ የፍርድ ቅጣት ያወርዳል ቁጣውም ምህረት የሌለበት ቁጣ ነው እናንተ ግን በአበው ቅዱሳን ተተክታቹኋል ከእግዚአብሔር ፊት ተገገርነታችሁን አታሳጉሉ ንፁሐን ሁናችሁ በደግነት ኑሩ በዚሁ በደብር ቅዱስ የሚወለድ እንደሌለም ዕወቁ ሕዝቦቹንም

ደብርቅዱስ ወኢመነ-ሂ እምአበው ዘይኄንን ሕዝቦ::

58. ወፈጺሞ ሄኖክ ዘንተ ነገረ ተመይጠ ውስተሕይወት
ወአንበሮ እግዚአብሔር አውዳ ለገነት ውስተብሔር ዘአልቦ
ውስቴታ ሞት:: ወእለተርፉ እምውሉደሴት ወረዱ
እምደብር ቅዱስ ኀበሐደረ ቃየል ወኢተርፉ
እምውስቴቶሙ ላእለደብር ቅዱስ ዘእንበለ ፫አበው ማቱሳላ
ላሜህ ወኖኅ::

59. ወዓቀበ ኖኅ በድንግልና ርእሶ ፭፻ ዓመተ ወእምዝ ተናገሮ
እግዚአብሔር መሐሪ ወአዘዞ ያውስብ ብእሲተ እንተስማ
ሃይከል ወለተናሙስ ወልደሄኖክ እሁሁ ለማቱሳላ::

60. ወከሰተ እግዚአብሔር ለኖኅ በእንተአይሁ ከመይመፅእ
ውስተዓለም ወየሐፅባ ለኩላ ምድር ወነገሮ ከመይከውን
ዝንቱ እምድሕረ ፻ ዓመት ወአዘዞ ይግበር ታቦተ
ለመድሐኒቱ ወመድሐኒተውሉዱ::

61. ወአዲ አዘዞ ይሞትር እምዕፀው እምላእለደብር ቅዱስ
ወአንበሮሙ ለዕፀው ውስተማሕደረውሉደቃየል በህየ
ይግበር ታቦተ ዘኑኅ ፫፻ በእመት ወግድሙ ፶ በእመት
ወቆሙ ወግድመርእሱ ፴ወ፩ በእመት::

62. ወይግበር ውስቴቱ ፫ ማሕደረ ከመይኩን ታሕታይ
ማሕደር ለአራዊት ወለእንስሣ ወማእከላይ ማሕደር

ለመምራት የሚችል በአበው አካሄድ ማንም አይኖርም::

58. ሄኖክ ይህንን ንግግሩ ሲጨርስ ወደሕይወት ተመለሰ
እግዚአብሔርም በገነት አደባባይ አስቀመጠው በዚሁም ሞት
የለም:: የቀሩት የሴት ልጆች ግን ማንም ሳያስገድዳቸው በሙሉ
ቃየል ወደሚኖርበት ምድር ተሟጥጠው ወረዱ ከነሱ ውስጥ
ማንም በደብር ቅዱስ አልቀረም ላሜህ ማቱሳላና ኖኅ ብቻ ቀሩ::

59. ጻድቁ ኖኅም በድንግልና ራሱን አምስት መቶ ዓመት ጠበቀ
ከዚህም የተነሳ እግዚአብሔር ኖኅን ሃይከል የተባለችውን የሄኖክ
ልጅ የማቱሳላ ወንድም ልጅ ናማስን እንዲያገባት አዘዘው::

60. እግዚአብሔር ስለአይህ አመጣጥም ገለፀለት የጥፋት ውሃ
ተነስቶ በዝሙት የረከሰችውን ዓለም እንደሚያጥባት ነገረው
ይህም ካንድ መቶ ዓመት በኋላ እንደሚፈፀም ገለፀለት ከወዲሁ
ጀምሮም ለራሱና ለቤተሰቡ ድሕነት መርከብን እንዲዘጋጅ አዘዘ::

61. እግዚአብሔር በድጋሚ ከደብር ቅዱስ ዛፎችን ይቈርጥ ዘንድ
አዘዘው እሱም ከደብረቅዱስ ቈርጦ በቃየል ልጆች ማደርያ
አስቀመጠው በዚሁም ሶስት መቶ ክንድ ርዝመት፣ ጐድኑ አምሳ
ክንድ የራሱ ጐድንና ቁመቱ ሰላሳ ክንድ የሆነ መርከብን
መሥራት ጀመረ::

62. በዚሁ መርከብ ውስጥ ሦስት ክፍሎችን ይሠራል ታችኛው
ክፍል ለአውሬዎችና ለእንስሳ ማደርያ ይሆናል መካከለኛው

ከመይኩን ሎቱ ወለብእሲቱ ወለውሉዱ ወለአንስቲያሆሙ ወይግበር ውስቴታ ሙዳየማይ ወመዛግብት ለሲሳይ ወይግበር ውስቴታ መጥቅዓ እምዕፀወሊባኖስ ዘኑኁ ፲እመት ወግድሙ ፩ እመት።

63. ወሶበአሐዘ ይግበር ታቦተ ይጠቅዕ ኩሎ ዕለተ ፲ጊዜ በነግህ ከመይትጋብኡ ለተግባሮሙ ወበጊዜ ቀትር ከመይትጋብኡ ለምሣሕ ወሶበየዓርብ ከመይትጋብኡ ውስተአብያቲሆሙ።

64. ወእመቦ ዘተሠእሎ በእንተተግባሩ ይነግሮ ከመእግዚአብሔር ይፌኑ ማየአይኅ ወየሐፅባ ለኩላ ምድር ውእቱሰ ይገብር ታቦተ ከመያድሕን ርእሶ ወብእሲቶ ወውሉዶ በውስቴታ።

65. ወሰምዓ ኖህ ትእዛዘእግዚአብሔር ወአውሰበ ብእሲተ ወእምድሕረ ፻ ዓመት ወለደ ውሉደ ፫ ተባዕተ ዘውእቶሙ ሴም ካም ወያፌት።

66. ወአውሰቡ አዋልዲሁ ለማቱሳላ ወሶበፈፀመ ኖኅ ገቢሮታ ለታቦት በከመአዘዞ እግዚአብሔር ማቱሳላ አሐዘ ለመዊት።

67. ወተጋብኡ ኀቤሁ ላሜህ ኖኅ ሴም ወካም ወአንስቲያሆሙ ወፀለየ ላእሌሆሙ ማቱሳላ ወባረከሙ ወአስተብቍአ

ክፍል ለራሱ ለሚስቱ፣ ለልጆቹና ለሚስቶቻቸው ይሆናል የውሃመጠራቀምያ ገንዳንም ሠራ ከዚሁም በተጨማሪ ሦስት ክንድ ርዝማኔና አንድ ክንድ ጐድን ያለው ደወል ከሊባኖስ ዕንጨት ሠራ።

63. መርከቡን በሚሠራበት ጊዜ ሁልጊዜ ጧት ጧት ለሥራ እንዲሠበሰቡ ደወል ይደውላል፣ ቀትር ሲሆን ምሳ ለመብላት እንዲሰበሰቡ ይደውላል ቀኑ አልፎ ምሽት ሲሆን ወደየቤታቸው እንዲገቡ ይደውላል።

64. መርከቡን ለምን እንደሚሠራው ጠያቂ ቢነሳበት እግዚአብሔር ይህቺን የረከሰች ምድር ለማጠብ የጥፋት ውሃን እንደሚያዘንምና፣ በዚሁም ምክንያት ራሱን ሚስቱን ልጆቹንና ሚስቶቻቸውን ለማዳን መርከብን እንዲሠራ መታዘዙን ይገልፅለታል።

65. ኖኅ የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ሰምቶ ሚስት አገባ ካገባ በአርባ ዓመቱ ሦስቱን ሴም ካምና ያፌትን ወለዳቸው ሦስቱን ወንዶች በቅደምተከተል ወለዳቸው።

66. የኖኅ ልጆች የማቱሳላ ልጆችን አገቡ ኖሕ እግዚአብሔር እንዳዘዘው የመርከቧን ሥራ እንደፈፀመ ማቱሳላ ሲሞት ተቃረበ።

67. ኖኅ ሴምና ያፌት ወደማቱሳላ ተሰበሰቡ ማቱሳላም በነሱ ላይና በሚስቶቻቸው ላይ ጸለየ ባረካቸውም ስለነሱም ወደእግዚአብሔር

በእንቲአሆሙ እንዘይብኪ ወየሐዝን ወይቤሎሙ አልቦ
ዘተርፈ ላእለ ዝንቱ ደብር ቅዱስ እምኵሎሙ አሕዛብ
ወኢመንሂ ዘእንበሌክሙ ወእግዚአብሔር አምላከአበዊነ
ዘፈጠሮ ለአቡነ አዳም ወለእምነ ሔዋን ወባረከ ላእሌሆሙ
ወመልአ ምድረ ዘርኦሙ።
68. ከማሁ ይባርክ ላእሌክሙ ወያብዝሕ ዘርአክሙ
ወይዕቀብክሙ ወይርአይክሙ ወያፅንዕክሙ ወየሀብክሙ
ሐይለ ወመዊዓ ወያድሕንክሙ እመቅሰፍት ዘይመፅእ
ላእለዛቲ ትውልድ ወይረሲ በረከታተ ላእለውሉድክሙ
ወውሉደውሉድክሙ ወየሀብክሙ ፀጋ ዘፀጋዎ
ለአቡነአዳም።
69. ወእሥእል ኀቤሁ ከመይፈኖ ኵሎ አዝርእቲክሙ
ወይፀጉክሙ መንግሥተ ወትንቢተ።
70. ወእሞዝ ይቤሎ ለኖኅ ኦ ቡሩክ እምኀበእግዚአብሔር
ስማዕ ቃልየ ወትእዛዝየ ወለቡ ከመእነ እወፅእ እምዝንቱ
ዓለም በከመወፅኡ አበው ቀደሞት።
71. [illegible] እግዚአብሔር ይፌኑ [illegible] ወየሐፅባ ለኵላ ምድር
በብዝሐ ሐጢአቶሙ ለሰብእ ወትድሕን አንተ ወውሉድከ
ወሶበሞትኩ ግንዘ ሥጋየ በከመገብሩ ላእለአበው ቀደምት
ወአንብረኒ ላእለአበው በአተመዛግብት።
72. ወእምድሕረዝ ንሣእ ብእሲተከ ወደቂቀከ ወአንሥቲያሆሙ

እያለቀሰ ማለደ እያዘነም "ከናንተ በቀር ከሁላቸው አህዛብ
መካከል በዚሁ በደብር ቅዱስ ማንም ሊቀር አልቻለም ያላችሁት
እናንተ ብቻ ናችሁ አባታችን አዳምንና እናታችን ሔዋንን የፈጠረ
እግዚአብሔር ምድርንም በዘራቸው ይሞሉዋት ዘንድ የባረከ እሱ
ነው፤ና።
68. እንዲሁም እግዚአብሔር እናንተን ይባርክ ዘራችሁም ያብዛ
እናንተንም ይጠብቅ ፅናቱንም ይሰጣችሁ ኀይልንና
አቸናፊነትንም ይስጣችሁ በዚችው ከእግዚአብሔር በወጣች
ትውልድ ሊመጣ ካለው መቅሰፍትም ይሠውራችሁ
በልጆቻችሁና በልጅልጆቻችሁም ላይ በረከቱን ያውርድ
ለአባታችን አዳም የሠጠውንም ፀጋ ለናንተም ይሥጥ"።
69. ስለናተም ወደእግዚአብሔር እለምናለሁ ዘራችሁ ሁሉ ይሞላ
ዘንድ መንግሥትና ትንቢትንም ለናንተ ይስጥ" አላቸው።
70. ኖህን ደግሞ እንዲህ አለው "ከእግዚአብሔር ዘንድ የተባረክህ
ኖሕ ሆይ ቃሌን ስማ ትእዛዜንም አክብር እኔ ከኔ የቀደሙት
አበው ከዚህ ዓለም እንደወጡ ከዚህ ዓለም እወጣለሁ።
71. እነሆ ሰዎች ብዙ ሐጢአት ስለሰሩበት እግዚአብሔር የጥፋትን
ውሃ ልኮ ምድርን ሊያጥባት ነው አንተና ቤተሰቦችህ ግን ከዚህ
የጥፋት ውሃ ትድናላችሁ እኔ ስሞት ለቀደሙት አበው
እንደተደረገው ሥጋየን ገንዘህ በቤተመዛግብት አኑረው።
72. ከዚህ በኋላ ሚስትህንና ልጆችህን የልጆችህም ሚስቶች ውሰድ

ወረድ እምደብር ቅዱስ ወንሣእ ምስሌከ ሥጋ አቡነ አዳም ወአንብር ውስተታቦት ዘአዘዘከ እግዚአብሔር ከመትግበራ ወአብእ ቁርባነ ወርቀ ከርቤ ወዕጣነ ዲበእንግድዓሁ። ወለእለሂ ተርፉ ሥጋሆሙ ለአበው አንብሮሙ ለፌ ወለፌ ከመይኩን ሥጋሁ ለአቡነ አዳም ማእከሎሙ ወረሲ ለከ ማሕደረከ።

73. ወለውሉድከ ውስተምሥራቀ ታቦት ወብእሲትከ ወአንስቲያሆሙ ለውሉድከ ወይሕድሩ ውስተምዕራብ ከመይትጋብኡ ለበሊዕ ወለስታይ ወለርእይ እስከአመትወፅእ እምታቦት። ወሶበተአተተ ማየአይሕ እምገፀምድር ወወፃእክሙ እምታቦት ወሐደርክሙ ውስተምድር አሜሃ ተጋብኡ ለበሊዕ ወለስታይ ወኢታዕርው ተቂንዮ ቅድመእግዚአብሔር ወቅድመሥጋሁ ለአዳም በፅድቅ ወበርትዕ፣ በንፅሕ ወበቅድስና።

74. ወእምድኅረወፃእክሙ እምታቦት ውእተ ጊዜ ንሣእ ወርቀ ወከርቤ ወዕጣነ ዘወፅአ እምውስተገነት ወአንብር ውስተ ምሥራቀ ምድር እንተተሐድር ውስቴታ ወእምከመ ጊዜ ፀአትከ እምዝ ዓለም አዝዞ ለወልድከ ሤም ይንሣእ ሥጋሁ ለአቡነ አዳም ወቅብሮ ውስተምድር።

75. እስመመካን ኀበተቀብረ ሥጋሁ በህየ ይከውን መድሐኒቱ

ከደብር ቅዱስም ውረድ ያባታችን አዳም ሥጋንም ካንተ ጋር ውሰድ እግዚአብሔር እንድትሠራት ካዘዘህ መርከብ ውስጥም አስቀምጣት ቁርባን ወርቅ፣ ከርቤና ዕጣንንም ከአዳም ሥጋ በላይ አስቀምጥ የቀሩትንም አበው ሥጋ ከደብር ቅዱስ አውርደህ በአዳም ሥጋ ግራናቀኝ አስቀምጠው የአባታችን አዳም ሥጋም በአበው ሥጋ ማሕል ይቀመጥ ለራስህም ማደርያ በመርከቧ ላይ ሥራ።

73. ከመርከቡ በስተምሥራቅ ክፍል ላንተና ለልጆችህ ለሚስትህም ለልጆችህም ሚስቶች ክፍል ትሠራለህ በስተምዕራቡም ክፍል መኖርያቸው ይሁን በዚሁ ለመብልና ለመጠጥ ይሰብሰቡ ከመርከቧ እስክትወጣ ድረስም ከዚሁ ሁናችሁ ወደውጭ ተመልከቱ የጥፋት ውሃ ከምድር ሲወገድ በምድር ስትኖሩ ያንጊዜ በሕብረት እየተሰበሰባችሁ ብሉ ጠጡ በእግዚአብሔር ፊትና በአዳም ሥጋ ፊትም በቅድስናና በንፅሕና፣ በቅንነትና በፅድቅ ከመገዛት ወደኋላ አትበሉ።

74. ከታቦት ከወጣችሁ በኋላ ያን ጊዜ ወርቅን ከርቤን፣ ዕጣንን (ከገነት የወጡ) ከምድር በስተምሥራቅ አስቀምጥ አንተም ከዚሁ ክፍል ከቤተሰቦችህ ጋር ትኖራለህ ከዚህ ዓለምም የምትለይበትን ጊዜ ሲደርስ ልጅህ ሴምን ያባታችን አዳምን ሥጋ ይውሰድና በምድር ላይ በክብር ቀብሮ ያስቀምጠው።

75. የአዳም ሥጋ በተቀበረበት ለልጅ ልጆቹ መድሐኒት ይሆናል

ወመድሐኒተ ውሉዱ በንበይትቀበር ሥጋሁ በህየ ፩ብእሲ እምውሉዱ ከመይትቀነይ ቅድመሥጋሁ ለአቡነ አዳም ወይግበር ክህነተ ቅድመ እግዚአብሔር ወይኩን ንፁሐ ኩሎ መዋዕለ ሕይወቱ።

76. ወአዝዞ ኢይስተይ ሜስ ወኢይክዓው ደመ ወኢይላጺ ርእሶ ወኢይምትር ፅፍሮ ወበህየ ኢያቅርብ ቁርባነ ዘእንስሳ አላ ይኩን መሥዋዕቱ ንፁሐ ሕብስተሥንዳሌ ወፍሬወይን።

77. ወናሁ መልአከ እግዚአብሔር የሐውር ቅድሜሁ ለዝንቱ ሕሩይ ብእሲ ያብፅሖ ውስተመካነ ዘድልው ይትቀበር ሥጋሁ ለአቡነአዳም ወአዲ አዝዞ ይኩን ልብሱ እምአነዳማእስእንስሳ እስመውእቱ ካህኑ ለእግዚአብሔር ዘሐረዮ ወቀደሶ።

78. ወፈጸሞ ማቱሳላ ዘንተ ትእዛዘ አንብዐ ወረደ እምብዝሐንዘኑ ወሞተ በእለተእሁድ አመ፩ ለመጋቢት ወኮነ መዋዕለ ሕይወቱ ፱፻፷ወ፱ ዓመት። ወገነዞ ወልዱ ላሜህ ወአንበሮ ውስተበዓተ መዛግብትንበ ሃለው አበው ቅዱሳን።

79. ወለሃው በእንቲአሁ ፵ ዕለተ ወእምድሕሬሁ ሐመ ላሜህ ወአዘዞ ለወልዱ ኖሕ በከመአዘዞ አቡሁ ማቱሳላ ወሞተ በሐሙስ ዕለት አመ፳ወ፩ ለመስከረም ወአመኮኖ ለሴም ፷ ወ ፲ ዓመት ወገነዞ ወልዱ ኖኅ ወአንበሮ ውስተበዓተ

በአዳም ሥጋም ላይ አንድ ቅዱስ ሰው እግዚአብሔርን በክህነት እያገለገለ ይኑር። ለአገልግሎት ይህ ሰው በንፅሕና በቅድስና ይኑር።

76. ጠጅ እንዳይጠጣ፣ ደም፣ እንዳያፈስ ራሱን እንዳይላጭ ጥፍሩንም እንዳይቆርጥ አዘዘው። በዚሁም የስንዴ ሕብስትንና ከወይን ፍሬ የተጨመቀ ወይን ብቻ ቁርባን እንዲያቀርብ ይሁን።

77. እነሆ አባታችን አዳም ሲቀበርበት ወደተዘጋጀው ያደርሰው ዘንድ የእግዚአብሔር መልአክ ከፊት ለፊቱ ይሄዳል ዳግመኛም ልብሱ ከእንስሳት ቁርበት የተሠራ ብቻ እንዲሆን አድርግ እስ እግዚአብሔር የመረጠውና የቀደሰው የእግዚአብሔር ካህን ነውና።

78. ይህን ሁሉ ትእዛዝ ተናግሮ በፈፀመ ጊዜ ማቱሳላ ከኀዘኑ ብዛት የተነሳ አለቀሰ እንባውም ወረደ በእለተእሁድ መጋቢት አንድ ቀንም ሞተ የሞተው በዘጠኝ መቶ ስድሳ ዘጠኝ ዓመቱ ነው ላሜህ ልጁ ገንዞ በቤተመዛግብት ቀበረው ቤተመዛግብቱ የቅዱሳን አበው ዓፅም ያረፈበት ነው።

79. ስለሱም አርባ ቀን አለቀሱ ከሱ በኋላ ላሜህ ታመመ ልጁ ኖኅንም አባቱ ማቱሳላ እንዳዘዘው አዘዘው። ላሜህ በዕለተ ሐሙስ መስከረም ሃያ አንድ ቀን የኖኅ ልጅ ሴም የስድሳ ስምንት ዓመት እያለ ሞተ ልጁ ኖኅም ገነዘው በቤተመዛግብትም

መዛግብት ወሐዘኑ በእንተአሁ ፺ ዕለተ ወተርፉ ኵሎሙ
አበው ምስለኖኅ ወልዱ ውስተደብር ቅዱስ፡፡

80. ወፀንሳ አዋልዲሁ ለቃየል እምውሉደሴት ወወለዳ ውሉደ ሐያላነ ወዕኑዓነ ዘይቤ መፅሐፍ ከመመላእክት ወረዱ ዲበምድር ወተደመሩ ምስለአንስት ዘኢኮነ ከማሁ፡፡

81. አላ ባህቱ ተብህለ ዝንቱ ነገር በእንተውሉደሴት ዘወረዱ እምደብር ቅዱስ ወተደመሩ ምስለአዋልዲሁ ለቃየል እስመእግዚአብሔር ልዑል ትካት ሰመዮሙ አማልክት አንትሙ ወደቂቀልዑል ኵልክሙ፡፡

82. ወሰበወረዱ እምደብር ቅዱስ ወተደመሩ ምስለአዋልዲሁ ለቃየል ወይቤ በእንቲአሆሙ አንሰ እቤ አማልክት አንትሙ ወደቂቀልዑል ኵልክሙ አንትሙሰ ከመሰብእ ትመውቱ ወከመአሐዱ እመላእክት ትወድቁ፡፡

83. ወለመንፈሳውያን ከመሰብእ ኢኮነፍጥረቶሙ ወአልቦ ላእሌሆሙ ፍትወተሥጋ ወሰበይሄሉ ላእሌሆሙ ፍትወተ ሥጋ ከመሰብእ እምኢሐደጉ አጋንንት ወኢአሐተኒ እምአንስት ወእምተደመሩ ምስሌሆን ወእምአማሰኑ ኵላ

ቀበረው ስለሱም ሕዝቦቹ አርባ ቀን አለቀሱ አበው በሙሉ እስከዚህ ጊዜ ድረስ ከኖኅ ጋር በደብር ቅዱስ ነበሩ፡፡

80. የቃየል ልጆች ከሴት ልጆች ልጆችን ወለዱ እነዚህም ልጆች እጅግ ሐይለኞች ሆኑ መጽሐፍ የሴት ልጆችን መላእክት ይላቸዋል ባልተፈቀደም መንገድ ሥጋዊውን ግንኙነት መፈፀማቸውን ይገልፃል፡፡

81. የሴት ልጆች የቃየልን ልጆች ዘፈን እየሰሙ በዓመፅ ቅድስናቸውን እየተው ወርዷል፡፡ ከቃየል ልጆች ጋርም በአመንዝራነት ግንኙነትን ፈፅመዋል ጥንት እግዚአብሔር የሴትን ልጆች እናንተ አማልክት ናችሁ የልዑልም ልጆች ናችሁ ብሏቸው ነበር፡፡

82. የሴት ልጆች በደብር ቅዱስ በነበሩ ጊዜ ንፁሐን በሐጢአት ያልተበከሉ ነበሩ ከደብር ቅዱስ ወርደው ከቃየል ልጆች ከተገናኙ በኋላ ግን እግዚአብሔር እኔስ አማልክት ናችሁ የልዑልም ልጆች ናችሁ ብያቸው ነበር በኋላ ግን እንደሰው ትሞታላችሁ ከመላእክት ተለይቶ እንደወደቀው ዲያብሉስም ትወድቃላችሁ አለ፡፡

83. ከመንፈስ የተፈጠሩ ሁሉ አፈጣጠራቸው እንደሰው አይደለም የሥጋ ፍትወትም የለባቸውም ፍትወተሥጋ በነሱ ላይ ቢኖር ኑሮ አጋንንት ሴቶችን እየተገናኙ በጨረሱዋቸው ነበር፡፡ በዚህም ዓለምን ሁሉ አንድም ሳያስቀሩ ለጥፋት አጋልጠው

ዓለሙ።

84. እስመአጋንንት ርኩሳን ነዮሙ ወያፈቅሩ አማስኖ ወዝሙተ ወሶበ ሥእኑ ለሊሆሙ ገቢሮታ ለዝሙት ይበውኡ ላእለሰብእ ወያስተጥዕሙ ሎሙ ዝሙተ ወርኩሰ ወፍትወተ እኪተ።

85. ወእምዝ ነሥአ ኖኅ ሥጋሁ ለአቡነ አዳም ወሥጋሆሙ ለኩሎሙ አበው ወአንበሮሙ ለኩሎሙ ዘዘዚአሁሙ ውስተታቦት ወፆረ ሴም ቁርባነ ዘወርቅ ወፆረ ካም ከርቤ ወፆረ ያፌት ዕጣነ ወተፈልጡ እምበዓተመዛግብት በዓቢይ ሐዘን ወብኪይ ወላህ።

86. ወእምዝ አንሥኡ አዕይንቲሆሙ ውስተገነት ገዓሩ ወበከዩ ወይቤሉ ሰላምለኪ ኦ ገነተትፍሥሕት ማህደሩ ለአቡነ አዳም ወይቤሉ አሌ ለነ እስመግእዝነ እምአገዋሪሁ ለገነት ወገባእነ ውስተምድር ርግምት ዘውስቴታ ፃዕር ወሕማም ወሐዘን።

87. ሰላም ለኪ ኦ በአተመዛግብት ማሕደረቅዱሳን ወንፁሐን ፍቁራኒሁ ለእግዚአብሔር ፀልዩ ላእሌነ ወባርኩነ ሰአሉ ወአስተብቁኡ በእንተ መድሐኒትነ ሰላም ለሴት ርእሰአበው ሰላም ለሄኖስ ዘናዘዞሙ ለሕዝቡ ሰላም

በጨረሱ ነበር።

84. አጋንንት የረከሱ ናቸው ጥፋትን ብቻ ይወዳሉ ዝሙትንም ይወዳሉ ዝሙትን መፈፀም ስለማይችሉም በሰው ላይ እያደሩ ሰውን ዝሙተኛ ያደርጉታል የረከሰውን ክፉውንና ፍትወትንም ያሠሩታል።

85. ከዚህ ቀጥሎ ኖኅ የአዳምን ሥጋና የሌሎችም አባቶች ሥጋ አሰባስቦ ወስዶ እየራሳቸውንም ለያይቶ አስቀመጣቸው በታቦትም ውስጥ አስገባቸው ሴም የቁርባኑን ወርቅ ተሸከመ ካም የከርቤውን ቁርባን ተሸከመ ያፌት የቁርባኑን ዕጣን ተሸከመ ሁሉም ከበዓተ መዛግብት በታላቅ ሐዘንና ልቅሶ ለመውጣት ተነሱ ወጥተውም ሄዱ።

86. ሲወጡ ሲዘጋጁም ዓይናቸውን ገልጠውና ቀና ብለው ወደገነት ተመለከቱ። አለቀሱም እያለቀሱም እንዲህ አሉ ገነት ሆይ ሰላም ላንቺ ይሁን የደስታ ቦታ ነሽና ያባታችን አዳም ማደርያ ነበርሽ ወዮልን እንዴት እንሁን ወደተረገመችው ምድር ልንሄድ ነው በዚች የተረገመች ምድር ሐዘን ጭንቅ በሽታና ደዌ ይበዛል።

87. ቤተመዛግብት ሆይ ሰላም ላንቺ ይሁን አንቺ የንፁሐን ቅዱሳን ማደርያ ነሽና የእግዚአብሔር ወዳጆች ባንቺ ይኖራሉ። የእግዚአብሔር ወዳጆች አበው ሆይ ስለኛ ፀልዩ ባርኩን ስለኛም ማልዱ ድሕነትን ናገኝ ዘንድ ለርእሰአበው ሴት ሰላም ሕዝቡን

ለቃይናን ወመላልኤል ዘፈትሐ ላእለሕዝቦሙ በዕድቅ ወበርትዕ።

88. ሰላም ለያሬድ ወለሄኖክ ወማቱሳላ ወላሜህ እለተቀንዩ ቅድመእግዚአብሔር በንዕሐ ወናንቀዓዱ ኀበኩሎሙ ከመይስአሉ ወያስተብቁኡ በእንተ መድሐኒትነ እስመናሁ ንወፅእ እምዝንቱ ማሕደር ወኢንሬእዮ ዳግመ እስከለዓለም።

89. ወእምዝ ወረዱ እምደብር ቅዱስ እንዘይስዕሙ አዕባኒሁ ወዕፀዊሁ በብካይ ወላህ ወበዓቢይ ሐዘን ወበዕሉ ውስተምድር።

90. ወአብአ ኖኅ ሥጋሁ ለአዳም ውስተታቦት ወአንበረ ማእከለ ወአንበረ ቁርባነ ዲበእንግድዓሁ በዓርብ እለት አመ ፲ወ፯ ለነሐሴ ወበሳኒታ አብአ ኩሎ አራዊተ ወእንሥሣ ውስተታሕቲት ማሕደር።

91. ወጊዜ ቀትር አብኦሙ ለአዕዋፍ ወለኩሉ ዘይሠርር ነፍስ ወአሕደሮሙ ውስተማእከላይ ማሕደር ወሰበየዓርብ ፀሐይ ቦኡ ኖኅ ወብእሲቱ ወደቂቁ ወአንስቲያሆሙ ወሐደሩ ውስተላዕላይ ማሕደር።

ያረጋጋ ሄኖስ ሰላም በእውነትና በቅንነት በሕዝቦቻቸው ላይ ለፈረዱ ቃይናንና መላልኤል ሰላም።

88. ለያሬድና ለሄኖክ ሰላም ለማቱሳላም ሰላም ለላሜህም ሰላም እነዚህ ሁሉ እግዚአብሔርን በንዕሕናና በቅድስና አገልግለውታል ወደሁላቸው ዓይናችንን እናጋጥጥ ስለኛ ድሕነት ይማልዱልን ዘንድ እነሆ ከዚህ ከተቀደሰው መኖርያ ልንወጣ ነው እስከዘለዓለምም ተመልሰን ይህን ቅዱስ ቦታ አናየውምና አሉ።

89. ከዚህ ጊዜ ጀምሮ ከደብርቅዱስ ለመውጣት ተነሱ የደብረቅዱስንም ዲንጋይና ዕንጨቱን እየተሳለሙ በታላቅ ልቅሶና ሐዘን ወጥተው ወደምድር ገቡ።

90. ኖኅ የአዳምን ሥጋ ከመርከቧ ማሕል አስቀመጠ ቁርባኑን ማለትም ከገነት ያመጡትን ወርቅ ከርቤና ዕጣን በአዳም ደረት ላይ አስቀመጠው ይህንንም በዕለተዓርብ ነሐሴ አሥራ ሰባት ቀን አደረገ በማግሥቱ አራዊቶቹን ሁሉ በታችኛው ክፍል አስገባ።

91. ቀትር ሲሆን ኖኅ ወፎችንና ሕይወት ያላቸውን በራሪዎች በሙሉ ወደመርከብ አስገብቶ በመካከለኛው ክፍል አኖራቸው ፀሐይ ሲጠልቅ ኖሕ ከሚስቱና ከልጆቹ ጋር ወደመርከቧ ገባ ከነሱ ጋርም በመሆን ከመርከባ ወደላይ በ3ኛው ደረጃ በተሠራው ክፍል ገቡ።

92. እስመ ታቦትሰ ተገብረት በአምሳለ ቤተክርስቲያን ዘአልቦ ውስቴታ ትእምርተ ተባእት ምስለአንስት ወአዲ ዘሀሎ ውስቴታ ዳሕን ወሰላም ከማሁ ኮነ ውስቴታ ፍቅር ወሰላም በማእከለአራዊት ወእንስሳ ወአዕዋፍ።

93. ወዘአብአ ኖኅ ውስቴታ እምዘቦ ነፍስ ኀዑሐን በበ፪ ዘውግ ወሶበአብአ ኖኅ ዘንተኩሎ ዓፀወ ዓናቅፀታቦት ወእምድሕረዝ ተርሕወ ሐዋሕወ ሰማይ ወወረዱ ዝናማት ወተሠጥቀት ምድር ወአውፅአት ማያተ ወፀለሉ ማያት መልዕልተ ምድር።

94. ወአስተርአየት ዓባይ ባሕር እንተ ስማ ሐኖስ ዘየአውዳ ለዓለም ወተፈነው ነፍሳት እምነኵለሄ ወሶበ ርእዩ ደቂቀሴት ዘንተ ኵሎ ጕዩ ኀበ ታቦት ወዓንቃዕደው ኀበኖህ ከመያብኦሙ ኀቤሁ

95. ውእቱሰ ኢያውሥኦሙ ወኢተናገሮሙ እስመ ታቦት ተገብረት ከመዝ ተዐፅወት ወተሐትመት በትእዛዘ እግዚአብሔር ውውእተ ጊዜ ነሥሑ ወሐዘኑ ወኢረከቡ ዘይረድኦሙ ወዘያድሕኖሙ እሙስና መሞቱ በከመዘመረ ዳዊት ነቢይ ወይቤ በእንቲአሆሙ አንሰእቤ

92. የኖኅ ታቦት (መርከብ ወንድና ሴት ብላ ልዩነት ባማታደርግ ቤተክርስቲያን ትመስላለች ወደቤተክርስቲያን የመጣ ሁሉ የእግዚአብሔርን ፍቅርና አንድነትን ያገኛል በቤተክርስቲያን መለየት የለም ለዚህም ምሳሌ ትሆን ዘንድ በኖሕ መርከብ ውስጥ የተለያዩ የዱር እንስሳትና አውሬዎች በሰላም ለመኖር ቻሉ ።

93. ኖኅ ሕይወት ካለው ተንቀሳቃሽ ሁሉ እየመረጠ ወደታቦት አስገባ በየስማቸውም ደረጃ አስቀመጣቸው ኖኅ ይህን ሁሉ አስገብቶ ከጨረሰ በኋላ የታቦቷን መስኮቶችና በሮች ዘጋ ከዚህ ጊዜ ጀምሮ የሰማይ መስኮቶች ተከፈቱ የጥፋት ዝናማትም መዝነም ጀመሩ ምድርም ተሰንጥቃ በውሃ ተጥለቀለቀች ውሆች በምድር ላይ ተንሳፈፉ።

94. ዓለም አንዲት ባሕር ሆነች ሐኖስ የሚባል ባሕርም ተፈጠረ ይህም ሐኖስ ዓለምን ሁሉ የሸፈነ ነው ነፍሳት ከየአቅጣጫው ተነሱ በቃኤል ልጆች የተጣሉ የሴት ልጆች ሮጡ ወደኖህ መርከብ አንጋጠጡ ኖሕንም እንዲያስገባቸው ከሩቅ ለመኑት

95. ኖህ ግን ለጩኸታቸውና ለዋይታቸው መልስ አልሠጠም ታቦቷ ሙሉ በሙሉ ሁለመናዋ ተዘግታለችና በእግዚአብሔር ትእዛዝ ማንም እንዳይገባባት ሁናለችና በዚህ ጊዜ አዘኑ ተፀፀቱ (ደቂቀ ሴት)ረዳትም አላገኙም ከጥፋትም የሚያድናቸው አላገኙም።

አማልክት አንትሙ ወደቂቀልዑል ኵልክሙ ፡፡

96. ወበዝንቱ ስም ዓቢይ ተሰመይክሙ ወዓለውክሙ ትእዛዘአበው ወገበርክምዋ ለሐጢአት ወአርኵስክሙ ሥጋክሙ ምስለአዋልደቃየል ናሁ ትመውቱ ኵልክሙ ወትትኰነኑ ምስለቀዳማዊ ዘወድቀ እምሰማይ፡፡

97. ወተለዓለት ታቦት ላእለኵሉ ገፀምድር ወማሰነኵሉ ውስተምድር በማየአይሕ ወተለዓሉ ማያት መልእክተ አርእስተአድባር መጠነ እመተ መንፈስ ቅዱስ አብፅሕዋ ወፆርዋ መዋግድ ለታቦት ታሕተ ገነተ ትፍሥሕት ወአፅነኑ መዋግድ አርእስቲሆሙ ወሰገዱ ለታቦት በቅድሜሃ ወእምዝ ተመይጡ ድሕረ፡፡

98. ወአማሰኑ ኵሎ ዘተርፈ ዲበምድር ወሰረረት ታቦት መልዕልተማያት በክንፈነፋስ እምሥራቅ እስከምዕራብ እምደቡብ እስከሰሜን አምሣለትእምርተ መስቀል ወነበሩ ማያት ላእለገፀ ምድር እንዘይበዝኑ ወይትወሰኩ ዕለተ

99. ወእምዝ ዓርመሙ ማያት ወአሐዘ ይተሀቱ በደሐራይ እስከቀዳሚቱ ለአይህ ወቆመት ታቦት ማእከለአድባር ዘይቤልዎሙ አድባረፍርዳ ወተፈልጡ ማያት ወገብኡ ውስተምዕላዳተሆሙ ወአሐዘ ይሕፅቡ በበንስቲት እስከ

96. በዚሁ ትልቅ ስም ተሰይማችሁ ነበር ቃል ግን ያባቶችን ትእዛዝ አፈረሳችሁ ሐጢአትንም ሠራችሁ ሥጋችሁን አረከሳችሁ በቃየል ልጆችም መንገድ ሄዳችሁ እነሆ ሁላችሁ ልታልቁ ነው አስቀድሞ ከሰማይ ከወደቀው ፍጡር ጋርም ፍዳችሁ ልትቀበሉ ነው፡፡

97. ከሁሉ ምድር በላይ ታቦት ከፍ አለች በምድር ያለውም ነፍስ ያለው ሁሉ ጠፋ በጥፋት ውሃም ተደመሰሰ ውኃዎች ከተራሮች በላይ ተንጣለሉ ከተራራዎች በላይ በመንፈስ ቅዱስ ክንድ አምስት ሆኑ የባሕር ሞገዶች ታቦቷን ከገነት ሥር አደረሱዋት ራሳቸውም ዝቅ አድርገው ወደሷ ከሰገዱ በኋላ ወደኋላቸው ተመለሱ

98. በምድር ያለውንና የቀረውንም ሁሉ አጠፉ የኖኅ ታቦት ከፍ ብላ ከውሃው በላይ በመሆን ከምሥራቅ ተነስታ ወደ ምሥራቅ ተንሳፈፈች እንደገና ከደቡብ ተነስታ ወደ ሰሜን ተንሳፈፈች ይህም የመስቀል ምልክት ነው ላንድ መቶ አምስት ቀናት ውሃዎች በመጨመር ላይ ነበሩ ሳያቋርጡም ይዘንቡ ነበር፡፡

99. ከዚህ በኋላ ግን ውሆች መጨመራቸውን አቆሙ ወደታች ዝቅ ይሉም ጀመር የመጀመሪያና የመጨረሻውን የጥፋት ውሃ በዚህ ቆመ ታቦት የፍርዳ ከሚባሉ ተራራዎች ማሕልም ቆመች ውሆችም ተለይተው ወደየመከማቻቸው ገቡ ቀስበቀስም እስከ

አመአሥሩ ወሰድሱ ለወርሐነሐሴ

100. በወርሐየካቲት ርእየ ኖሕ አርእስተ አድባር እምውስተታቦት አመአሥሩ ለወርኀ መጋቢት ወአርሐወ ኖኅ ሆሕተ ታቦት ዘመንገለ ምሥራቅ ወፈነዎ ለቋል ከመያእምር ዜና ውእቱሰ ኢተመይጠ ወኢገብአ ኀቤሁ።

101. ወዳግመ ፈነዋ ለርግብ ወሖረት ወኦደታ ለምድር ወኢረከበት መካነ ኀበተዓርፍ ወተመይጠት ሶበየዓርብ ፀሐይ ወእምድሕረ ሰቡል መዋዕል ዳግመ ፈነዋ ለርግብ ወሖረት ወእምዝ ተመይጠት ወገብአት ምስለቈፅ ለዘይት ወሐመልሚል።

102. እምርግብ ይትአወቅ ምስጢረቅድሳት አስመቀዳሚት ርግብ ትመስል ቀዳሚት ትእዛዝ ወኢረከበት ዕረፍተ እምኀበ አሕዛብ እኩያን።

103. ወዳግሚት ትመስል ዘረከበት ዕረፍተ ኀበአሕዛብ ዘተወከፉ ምሥጢራተጥምቀት ዘሰበኩ ምፅአቶ ለክርስቶስ።

104. ወሐለፈ ሚያዝያ በእለተእሁድ ተአተተ ማየአይህ እምላእለገፀምድር ወአስተርአየ የብስ ወበዛቲ እለት ወፅአ ኖሕ ወብእሲቱ ወደቂቁ ወአንስቲያሆሙ እምታቦት

ነሐሴ 16 ድረስ ወደ ምድር ሰረገ።

100. በየካቲት ወር ኖኅ የተራሮችን ጫፍ ለማየት ቻለ መጋቢት አሥር ቀን ኖኅ የታቦቷን መስኮቶች ከወደምሥራቅ አቅጣጫ ከፍቶ ቍራንም በዚሁ መስኮት አስወጥቶ ላከው የምድርን ሁናቴ ይመለከት ዘንድ እሱ ግን አልተመለሰም እንደ ወጣ ቀረ ።

101. ኖኅ ዳግም ርግብን ላካት እሷም ተልእኮዋን ለመፈፀም ሄደች ምድር ላይ ዞረች የምታርፋትንም ደረቅ ቦታ ስላጣች ሲመሽ ተመልሳ ገባች እንደገና ሰባት ቀን ቆይቶ ኖኅ ርግብን ላካት ተልእኮዋን አከናውና የዘይቱን የለመለመ ቅጠል ይዛ ተመለሰች

102. ከክፋዎችና የተረገሙ ከሕዛብ ዘንድ በቅድምያ የእግዚአብሔር ትእዛዝ ተቀባይነትን አለማግኘቷ ከርግቧ ማረፊያ ባለማግኘቷ ይተረጕማል።

103. ሁለተኛዋ የርግብ ማረፍያ ማግኘት ደግሞ የእግዚአብሔር ትእዛዝ የጥምቀትን ምሥጢራት ተቀብለው የወልደ እግዚአብሔርን ወደዚህ ዓለም መምጣት የሰበኩና የፃድቁ ኖሕ ስድስት መቶ ዓመት ዘመን ፍፃሜን ትርጓሜ ያስረዳል።

104. የሚያዝያ ወር አልፎ በእለተ እሁድ የጥፋት ውሃ ከምድር ተወገደ በምትኩም ደረቅ መሬት (የብስ) ታየ በዚችው እለት ኖኅ ከሚስቱ ጋር ከልጆቹ ጋርና ከልጅ ልጆቹ ሚስቶች ጋር በሕብረት ከታቦቱ ወጡ።

105. ወአውፅአሙ ለኩሉሙ አራዊት ወእንስሳ ወአዕዋፍ ወኩሉ ፍጥረት ዘነበሩ ውስተታቦት አመሰብዑ ለወርሐሚያዝያ ወሐነፀ ኖሕ ወደቀቁ ሀገረ ወሰመዩዋ ንማቁ.

106. ወሀለወት ይእቲ ሀገር ጐለቆሙ ለእለነበሩ ውስተታቦት ምስለኖህ ነፍስ ወእንስሳ ወሐነፀ ኖኅ ምሥዋአ ለእግዚአብሔር ወአብአ መሥዋእተ እምእንስሳ ወአዕዋፍ ንፁሐን ወተወክፈ እግዚአብሔር መሥዋእቶ ወተካየደ ምስሌሁ ኪዳነ ከመኢያውርድ ዳግመ ማየአይህ ዲበምድር እስከለዓለም

107. እግዚአብሔር ልውል መልእልተ ደመና ተከለ ቀስተደመና ዘምሐረት ቀስተደመና አርአየ እስመእም ቅድም ነበሩ አሕዛብ ይሬእዩ ቀስተመቅሥፍተ መዓቱ።

108. ወተከሉ ውሉደኖሕ ዐፀደ ውስተሀገር ወገብሩ እምፍሬ ሐዲስ ሜሰ ወአስተዩዎ ለኖኅ ሠክረ ኖኅ ወኖመ ወተከስተ ዕራቁ እስመቀዲሙ ኢየአምርስቴወይን።

109. ወሰበርእየ ወልዱ ካም ስሐቀ ላእሌሁ ወፀውዖሙ

105. ኖኅ ሰዎቹን ካወጣ በኋላ የዱርአውሬዎቹን እንስሳቱን ወፎቹንና ሌሎችንም ፍጥረታት ከነበሩበት የታባቱ ታችኛው ክፍል አስወጣቸው ኖኅና ልጆቹ አገርን ቈረቈሩ "ንማቁ" ብለውም ሰየሟት

106. አቺም አገር ለብዙ ጊዜ ኖረች ኖኅ ከታቦት ውስጥ የወጡትን እንስሳትንና ሰዎችን ቈጠራቸው ኖኅ ከዚህ በመቀጠል ለእግዚአብሔር መሥዋእት የሚያቀርብበትን መሠዊያ ሠራ የእንስሳትንና የወፎችንም ንፁሕ መሥዋእት ለእግዚአብሔር አቀረበ እግዚአብሔርም መሥዋዕቱን ተቀበለ ዳግም በጥፋት ውሃ ምድርን እስከዘለዓለም እንደማያጠፋትም ለኖህ ቃልኪዳን ገባለት

107. እግዚአብሔር የመዓት ምልክት በደመና ላይ ይታይ የነበረውን አስወገደ ከጥፋት ውኃ በፊት የምድር አሕዛብ ከደመና ላይ የእግዚአብሔር የቁጣ ምልክት የሆነውን ዝናም በዘነመ ቁጥር ይመለከቱ ነበር ኖኅ ከእግዚአብሔር ጋር ቃለኪዳን ከገባ በኃላ ግን ቀረ።

108. የኖኅ ልጆች የወይን ቦታን አዘጋጅተው ወይንን አመረቱ ከወይኑም የወይን ጠጅን አዘጋጁና ለኖሕ አጠጡት እሱም ከዚህ በፊት ወይን ጠጅን ጠጥቶ ስለማያውቅ ሰክሮ ተኛ ዕራቁቱንም ሆነ

109. ልጁ ካም የኖሕን ወይን ጠጥቶ በሥካር መያዝ አይቶ ሳቀ

ለአሐዊሁ ከመይርአዩ ሐፍረቶ ለአቡሆሙ ወሶበርእዩ ሴም ወያፌት ዘከመ ተከሥተ ሕፍረተአቡሆሙ ድንገፁ ዓቢየ ድንጋፄ ወነሥኡ ልብሰ ወሰፍሑ ዲበመታክፍቲሆሙ ወሆሩ ድሕሪተ ከመኢይርአዩ ሐፍረተ አቡሆሙ

110. መነቂሆ ኖሕ እምንዋመ ሥካሩ ዜነውዎ ብእሲቱ ኵሎ ዘከመገብሩ ደቂቁ መተምዕዐ ላእለ ወልዱ ካም ወይቤ ርጉመ ለይኩን ከነዓን ወይኩኑ ደቂቁ አግብርተ ለአሐዊሁ እስከዘለዓለም።

111. ወበእንተዝ ኮኑ አግብርተ ደቂቀካም ለደቂቀሴም ወያፌት ወነበረ ካም ኩሎ መዋዕለሕይወቱ በዕልወት እንዘያፈቅር እኩየ ፍትወተ በእንተዘተሳለቀ ላእለአቡሁ ወኮነ ንዋመሥካሩ ለኖኅ ምስለሥቅለቱ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወንዋሙ ውስተመቃብር ሰለስተ መዋዕለ በከመዘመረ ዳዊት ነቢይ ወተንሥአ እግዚአብሔር ከመዘንቃሕ እምንዋም ወከመኃያል ወሕዳገወይን።

112. ወሶበተንስአ እመቃብሩ ረገሞ ለሠይጣን ወአማሰኖሙ ለእለስቀልዎ ወዘረዎሙ ውስተኵሉ ዓለም ወከማሁ ኮኑ ውለደከነዓን አግብረተ እስከለዓለም ወይትቀነዩ ለአኃእዝቲሆሙ ወይከውኑ ነዳያነ ወይሰመዩ አግብርቲሆሙ ለአግብርት።

ወንድሞቹ ሴምንና ያፌትንም ጠራቸው ያባታቸውን ዕራቁቱ መሆን ተመልክተው እጅግ ደነገጡ ልብስንም አምጥተው በትክሻና በትከሻቸው በመዘርጋት ያባታቸውን ዕራቁትነት ላለማየት የኋሊት በመሄድ አለባበሱት

110. ኖሕ በነቃ ጊዜ በሱ ላይ ካም እንደሳቀና ሌሎቹ ልጆቹ ግን ዕራቁትነቱን እንደሸፈኑ ሚስቱ ነገረችው በዚህ ጊዜ ኖኅ እጅግ ተናደደ እንዲህም አለ ካም የተረገመ ይሁን ልጆቹም በሱ ጥፋት ለወንዱሞቹ ባሮች ይሁኑ።

111. የካም ልጆች ከዚሁ በተነሳ ምክንያት ለወንድሞቹ ባሮች ሆኑ ካም መላ የሕይወት ዘመኑ በዓመፅና የረከሰውን ነገር በመፈፀም ኖረ በባቱ ዕራቁትነት ዘብቷልና የኖኅ በሥካር መተኛትም ከጌታ ሥቅለት ጋር ያገናኙታል እንዲሁም ከጌታ ትንሣኤ ጋር በምሥጢር ይገናኛል ዳዊትም እግዚአብሔር ከእንቅልፍ እንደመነሳት ባለ አኳኋን ከሙታን ተለይቶ ተነሳ ብሏል።

112. ኢየሱስ ክርስቶስ ከመቃብር ከተነሳ በኋላ የሠይጣንን ኃይል ሠብሯልና የሰቀሉትንም አይሁድ በመላዓለም ተበታትነው ካገራቸውም ተነቅለው እንዲቀሩ አድርጓልና በሄዱበትም አገር ለወንድሞቻቸውና ለጌቶቻቸው እንዲገዙና በድሕነትም እንዲንከራተቱ ሁኗል።

113. ወሐይወ ኖሕ እምድሕረወፅአ እምታቦት ፫፻ወ፶ ዓመተ ወሶበ በፅሐ ጊዜፍልሰቱ፡ እምዝንቱ፡ ዓለም ተጋብኡ ኀቤሁ ሴም ወካም ወአርፋክስድ ወፋሌቅ ወፀለየ ላእሌሆሙ ወባረኮሙ ወአስተበቍዐ ላእሌሆሙ፡፡

114. ወአዘዞ ለሴም ወልዱ ወበኵሩ በሕቡእ ወይቤሎ ቅብር ሥጋየ ውስተ ምድር ወባእ ውስተታቦተመድሐኒት ወአውፅዕ እምኔሁ ሥጋሁ ለአዳም በሕቡእ ወኢያእምርከ ወኢመኑሂ ወአስተዳሉ ስርእስከ ስንቀ ወንሥእ ምስሌከ ለመልከጼዴቅ እስመሐረዮ እግዚአብሔር እምኵሎሙ ውሉድክሙ ወዑር ምስሌከ ሥጋሁ ለአቡነ አዳም፡፡

115. ወሶበ በጻሕከ ማእከለምድር ህየ ቅብር ሥጋሁ ለአቡነ አዳም ወአንብሮ ለመልከጼዴቅ ውስተ ውእቱ መካነ ከመይትቀነይ ቅድመ ሥጋሁ ለአቡነ አዳም ወናሁ መልአከ እግዚአብሔር የሐውር ቅድሜክሙ ወይመርሐክሙ ኀበውእቱ መካነ ማእከለምድር ዘስሙ ጎልጎታ ወበህየ ያስተርኢ ሐይለእግዚአብሔር፡፡

116. እስመ ፬ መዓዝኒሁ ለዓለም ይከውን ፩ ማእዘንተ ወበህየ ይከውን መድሐኒተውሉዱ ዝንቱስ ፅሑፍ ውስተፅላተ ዘእብን ዘነሥአ ሙሴ እምእደዊሁ ለእግዚአብሔር

117. ወፈድፋደ አዘዞ ኖኅ ለሴም ከመይዕቀብ ዘንተ ትእዛዘ

113. ከጥፋት ውሃ በኋላ ኖሕ ሦስት መቶ አምሳ ዓመት ኖረ ከዚህ ዓለም የሚለይበት ጊዜ ሲደርስ ሴም፣ ካም፣ ያፌት አርፋክስድና ፋሌቅ ወደሱ ተሰበሰቡ እሱም ፀለየላቸው ባረካቸው ስለነሱም ወደእግዚአብሔር ማለደ፡፡

114. ልጁንም ሴም እንዲህ ሲል አዘዘው ሥጋየን በምድር ቅበር ወደመዳኛዋም ታቦት ግባና ማንም ሳያይህ የአዳም አባታችንን ሥጋ አውጣው ስንቅንም አዘጋጅ ይህንንም ማንም አይወቅ መልከጼዴቅንም ካንተጋር ውሰደው ከናንተ ሁሉ አብልጦ እግዚአብሔር መርጦታልና አንተም ያባታችን አዳምን ሥጋ ተሸከም፡፡

115. በምድር ማሕል ስትደርስ በዚሁ የአባታችንን አዳም ሥጋ ቅበር መልከ ጼዴቅንም አዳም በተቀበረበት ቦታ አስቀምጠው ከአዳም ሥጋ ፊት ለእግዚአብሔር ይገዛ ዘንድ ወደምድር ማህል ስትጓዙ የእግዚአብሔር መልአክ ይመራቿኋል ከፊት ለፊታችሁ እየተጓዘም ጎልጎታ ከተባለው ቦታ ያደርሳቿኋል በዚህም የእግዚአብሔር ሐይል ይታያል፡፡

116. የዓለም መአዝን አራት መሆኑ ሲታወቅ አራት መሆኑ ቀርቶ አንድ ይሆናል በዚህም ጊዜ የአዳም ልጆች ድሕነት ይሆናል ይህም ሙሴ ከእግዚአብሔር በተቀበላት የዲንጋይ ፅላት ውስጥ ተፅፎ ነበር፡፡

117. በይበልጥ ግን ይህን ትእዛዝ አጥብቆ እንዲጠብቅ አጥብቆ

ወአዲ ይቤሉ ከመዛቲ ትእዛዝ አዘዘ አዳም ለሴት ወሴት ለሄኖስ ወሄኖስ ለቃይናን ወቃይናን ለመላልኤል ወመላልኤል ለያሬድ ወያሬድ ለሄኖክ ወሄኖክ ለማቱሳላ ወማቱሳላ ለላሜህ ወላሜህ ለኖኅ።

118. ወአምሐሎ ኖሕ ለሴም ወልዱ ከመኢድንግር በእንተሥጋሁ ለአዳም ወኢለመኑሂ ወፈፂሞ ኖኅ ዘንተ ትእዛዘ ሞተ በረቡዕ ዕለት አመ፳ ለወርሐ ጥር ወገነዞ ወልዱ ሴም ወቀበሮ ውስተምድር ወሐዘኑ በእንቲአሁ በብካይ ወላህ ፵ ዕለተ ወኮነ ኩሉ መዋዕለ ሕይወቱ ለኖኅ ፱፻ ወ፶ ዓመተ።

119. ወእምድሕረዝ ቦአ ሴም ውስተ ታቦት በሕቡዕ ወአውፅአ እምኔሁ ሥጋሁ ለአዳም ወሐተማ ለታቦት በማሕተመ አቡሁ ወበማሕተሙ ወፀውዖሙ ለካም ወያፌት አዘዘኒ ወይቤሎሙ አእምሩኬ ከመአቡየ ኖኅ እምቅድመይሙት ወይቤለኒ ሑር ውስተምድር ልዕልት ወውድ ወስቴታ ከመአእምር ዕፀወ ወፍሬያተ ወፈውሰ ዘሐለወ ህየ።

120. ወናሁ አሐድግ ብእሲትየ ወውሉድየ ዕቀብዎሙ ፈድፋደ እስከእገብእ ኀቤክሙ።

121. ወይቤልዎ ለእመትፈቅድ ትግበር ከመንንሣእ ምስሌከ ብዙሐን ብዙሐን ሰብአ አስመምድር ኀበተሐውር ሐለው ብዙሐን

አዘዘው እንዲህም አለው ይህን ትእዛዝ አዳም ለሴት ሴት ለሄኖስ፣ ሄኖስ ለቃይናንን ቃይናን ለመላልኤል መላልኤል ለያሬድ ያሬድ ለሄኖክ ሄኖክ ለማቱሳላ ማቱሳላ ለላሜህ ላሜህ ለራሱ ለኖኅ የተላለፈ ነው።

118. ኖህ ሴሞን ለማንም አዳም የተቀበረበትን ቦታ እንዳያሳይ አስማለው ኖኅ ይህንን ሁሉ ተናግሮ ሲያበቃ ጥር ስድስት ቀን በዕለተ ረቡዕ ሞተ ልጁ ሴምም ገንዞ በምድር ላይ ቀበረው ስለኖኅ ሞት ወገኖቹ አርባ ቀን ሙሉ በታላቅ ሐዘን አለቀሱ የኖኅ ጠቅላላ ዕድሜ ዘጠኝ መቶ አምሳ ዓመት ነው።

119. ከዚህ በኋላ ኖሕ በድብቅ ወደታቦት ገባና የአዳምን ሥጋ አወጣ። ባባቱ ማሕተምና በራሱ ማሕተም ታቦቷን አተመ ካምንና ያፌትንም ጠርቶ "አባቴ ኖኅ ሊሞት በተቃረበ ጊዜ ያዘዘኝን ሁሉ እወቁ እንዲህም አለኝ ወደከፍተኛው ቦታ ሂድ እየተዘዋወርክም ተመልከታት በሷ ውስጥ ያሉትን ፍራፍሬዎችንና ለሰው ልጅ መድሐኒት ሊሆኑ የሚችሉትን ዕፀዋት አውቅ ዘንድ።

120. እነሆ ሚስቴንና ልጆቼን ትቼ እሄዳለሁ እናንተ በጥንቃቄ ጠብቁዋቸው አላቸው።

121. እነሱም "ይህን የምትለውን የምትፈፅም ከሆነ ብዙ ሰውን አስከትለህ ሂድ የምትሄድበት ቦታ ብዙ አንበሶችና ነብሮች

አራዊት ወአናብስት።

122. ወይቤሎሙ መልአከእግዚአብሔር የሐውር ምስሌየ ወውእቱ የዓቅበኒ ወአስተብቍዑ ሎቱ አሐዊሁ ወይቤልዎ እግዚአብሔር አምላከ አበዊነ የሀሉ ምስሌከ ወያድሕንከ ወይምራሕከ በኵሉ ፍናዊከ።

123. ወእምዝ ይቤሎሙ አእምሩኬ ከመአቡየ ኖኅ አምሐለኒ እምቅድመይሙት ወአዘዘኒ ከመኢይበውእ ውስተታቦት አነኒ ወባዕድኒ ወናሁ ሐተምክዋ በማሕተመ አቡየ ወበማሕተመዚአየ ይእዜኒ ዑቁ ከመኢይባእ ወኢ፩ እምኔክሙ ወኢውሉድክሙ።

124. ወይቤልዎ ኦሆ ንትኤዘዝ ለቃልከ ወለትእዛዘ አቡነ ወእምዝ ሖረ ሴም ኀበአቡሁ ወእሙ ለመልከጼዴቅ ወይቤሎሙ እፈቅድ ከመመልከጼዴቅ ይናዝዘኒ በውስተፍኖት ወይቤልዎ ነዋ ቅድሜከ ግበር ላእሌሁ በከመፈቀድከ።

125. ወእምዝ ፀውአ ሴም ለመልከጼዴቅ ሌሊተ ወፆረ ምስሌሁ ሥጋሁ ለአቡነ አዳም ወወፅኡ ወመልአከ እግዚአብሔር ቅድሜሆሙ ወአብፅሖሙ ኀበውእቱ መካን ፍጡነ ወይቤሎሙ ናሁ በፃሕክሙ እስመዝንቱ መካን።

126. ወተሰጥቀት ምድር በአምሳለ ሆሕት ወመሠጠቶ

ያሉበት ነውና” አሉት።

122. ሴም ሲመልስላቸው እንዲህ አላቸው “የእግዚአብሔር መልአክ ከኔ ጋር ይሄዳል። እሱም ከአውሬዎች አፍ ይጠብቀኛል”። ከዚህ በኋላ ማለዱት እንዲህም አሉት “የአባቶቻችን አምላክ ካንተ ጋር ይሁን አይለይህ”።

123. ሴም ለወንድሞቹ እንዲህ አላቸው “አስተውሉ አባቴ ኖኅ ሊሞት በተቃረበ ጊዜ ከኔ ጀምሮ ማንም ወደታቦት እንዳይገባ በጥብቅ አስጠንቅቆ አስምሎኛል እኔም ባባቴ ኖሕና በራሴ ማሕተም አትሜአት አለሁ ስለዚህ እናንተም ሆናችሁ ልጆቻችሁ አንድም ሰው ወደታቦት ለመግባት እንዳይሞክር ተጠንቀቁ።”

124. እነሱም እሺ ለቃልህና ላባታችን ኖኅ ትእዛዝ እንታዘዘለን አሉት ቀጥሎ ሴም ወደመልከጼዴቅ አባትና እናት ሄዶ መልከጼዴቅ ይሠጡት ዘንድ ጠየቃቸው እነሱም መልከጼዴቅ ካንተፊት ነው እንደፈቀድህ አድርገው አሉት።

125. መልከጼዴቅን ሴም በሌሊት ጠራው ከሱም ጋር የአባታችንን አዳም ሥጋ ተሸክመው ጉዞ ቀጠሉ መልአከእግዚአብሔርም እየመራቸው ወደማእከለምድር አደረሳቸው ማእከለምድር የተባለውን ቦታም ይህ ነው በማለት አስረድቶ ነገራቸው።

126. ምድር በመስኮት አምሳል ተሠነጠቀች የአዳምንም ሥጋ

ለውእቱ ሥጋ ወተሐትመት ለሊሃ ወገብአት ከመቀዳሚ ወሥሙ ለውእቱ መካን ጎልጎታ እስመሀየ አንበሩ ርእስአቡሆሙ ለኵሉ ፍጥረት ወሀየ ነበረ ርእሰ ከይሲ።።

127. ወነበረ ርእሰ ከይሲ ዘአስሐቶ ለአዳም ወአዲ ሰሙ ለውእቱ መካን ሉጦዴዬ ዘበትርጊሜሁ ኵሎሙ ሕዝብ ብሂል እስመበሀየ ይትጋብኡ ኵሎሙ ፍጡራን ወይቤሎ ሴም ለመልከጼዴቅ አንተ ካህኑ ለዓለም።።

128. ይእዜኒ አእኵቶ ለእግዚአብሔር አምላክከ ዘሐረየከ ለክህነት ቅድሜሁ ወኢትትፈለጥ እምዝንቱ መካን እስከለዓለም ወኢታውስብ ብእሲተ ወኢትላፂ ርእሰከ ወኢትምትር ፅፍረከ ወኢትክዓው ደመ ወኢትሕንፅ ቤተ መልእልተ መካን ወኢትሱእ መሥዋዕተ ዘእንሥሣ።።

129. ዳእሙ ይኩን መሥዋእትከ ሕብስተስንዳሌ ንፁሕ ቅድመ እግዚአብሔር ወእምፍሬወይን ንፁሕ ወናሁ መልአከ እግዚአብሔር ይሃሉ ምስሌከ እስከለዓለም።።

130. ሴም ሰዓሞ ለመልከጼዴቅ ወሐደጎ ውስተውእቱ መካን።።

131. ወተመይጠ ሴም ወገብአ ውስተ ማሕደሩ ወመፅኡ ኀቤሁ ኢዮሰዴቅ ወፋሌቅ አቡሁ ለመልከጼዴቅ ወይቤሎሙ መልከጼዴቅ ሐመ በፍኖት ወሞተ ወአነ ቀበርክዎ።።

አስገብታ በገዛ ራስዋ እንደወትሮዋ ተዘጋች የጎልጎታም ቦታ እንዲሁ ሆነ ከዚህም ጊዜ ጀምሮ የፍጥረቶች ራስ በዚሁ አኖሩ የከይሲም ራስ በዚሁ ነበር።።

127. ይህ ከይሲ አዳምንና ሄዋንን ያሳተ ነው የዚሁ ቦታ ስም ሉጦዴዬ ይባላል ትርጓሜውም ህዝብ ሁላቸው ማለት ነው ፍጡራን ሁሉ ለወደፊቱ በዚሁ ይሰበሰባሉና ሴም መልከዼዴቅን አንተ የዓለም ካህን ነህ አለው።።

128. ዛሬ አንተን የመረጠ እግዚአብሔርን አመሰግነዋለሁ እሱ ለክህነት መርጦሃል እስከመጨረሻው ድረስ ከዚህ ቦታ አትለይ ሚስት አታግባ የራስሕንም ጠጉር አትላጭ ጥፍርህንም አትቊረጥ ደምን አታፍስስ በዚህ ዓለም የምትኖርበትንም ቤት ለመሥራት አትሞክር የእንሥሣትን መሥዋዕት አትሠዋ።።

129. ነገር ግን ከእግዚአብሔር ፊት የሚቀርበው መሥዋእትህ ንፁሕ የስንዴ ሕብስትና ከወይን ፍሬ ይሁን የእግዚአብሔር መልአክም እስከዘለዓለም ካንተ ሳይለይ ይኖራል።።

130. ሴም መልከጼዴቅን ከመካነጎልጎታ ካደረሰው በኋላ ሳመውና ከቦታው ትቶት ሄደ።።

131. ሴም መልከጼደቅን የኣዳም ሥጋ እንዲያገለግል ካስቀመጠው በኋላ ተመለሰ ወደሱም የመልከጼዴቅ አባት ፋሌቅና ኢዮሰዴቅ መጡ ሴምም መልከዼዴቅ ከመንገድ ታሞ ስለሞተ ቀበርኩት አላቸው።።

132. ወሰሚዖሙ ዘንተ ነገረ አቡሁ ወአዝማዲሁ ሐዘኑ በእንቲአሁ ዓቢየ ሐዘነ፡፡

133. ወሶበኮኖ ለሴም ጻድቅ ፫፻ ዓመት ሞተ ወገነዞ ወልዱ አርፋክስድ ወቀበሮ ወሶበ ኮኖ ለአርፋክስድ ፬፻ ወ፫ ዓመት ሞተ ወገነዞ ሳላ ወልዱ ወቀበሮ ውስተ ሀገር ዘሐነፃ አርፋክስድ ወሰመያ አርናሳዊት፡፡

134. ወሶበኮኖ ለሳላ ፬፻ ዓመት ወሞተ ወቀበሮ ቦዔር ወልዱ ውስተ ሀገር ዘሐነፃ ሳላ ጥቃ ስንካርብ፡፡ ወሶበኮኖ ለቦዔር ፬፻ ፵ወ፯ ዓመት ሞተ ወቀበሮ ወልዱ ፋሌቅ ውስተዘሐነፀ ቦኤር ወሰመያ በስመዚአሁ፡፡

135. ወሶበኮኖ ለፋሌቅ ፬፻ወ ፴ ዓመት ሞተ ውእቱኒ ወገነዞ ወልዱ ራግው ወቀበሮ ወሰበኮኖ ለራግው ፪፻ወ፴ ዓመት ተጋብኡ ኵሎሙ ትውልደሴም ወካም ወያፌት ወሖሩ ውስተምድር ልዕልት ኀበመካነ ዘስሙ ንስቆባቁእ፡፡

136. ወነበሩ ህየ ወይትናገሩ ኵሎሙ በነገረሱርያን ወበልሳነ ዕርዕ ወበነገረ ከላዳውያን እስመነገሩ ዘይቤሉ ለአዳም በነገረ ዕብራውያን ሐሰው፡፡

137. እስመእስይቀውሙ በየማነ እግዚአብሔር ይትናገሩ በነገረሱርስት፡፡

132. አባቱና መላ ቤተሰቦቹ የመልከጼዴቅን መሞት ሰምተው እጅግ አዘኑ፡፡

133. ሴም ሦስት መቶ ዓመት ሲሞላው ሞተ ልጁ አርፋክስድ ገንዞ ቀበረው አርፋክስድም በአራት መቶ አምስት ዓመቱ ሞተ ልጁ ሳላም ገንዞ አርፋክስድ በሠራት አገር ቀበረው፡፡ አርፋክስድ የተቀበረባት ቦታ አርናሳዊት ተባለች፡፡

134. ሳላ አራት መቶ ዓመት ሲሞላው ሞተ ልጁ ቦኤርሞ ራሱ ሳላ ባነፀው ቦታ ቀበረው ይህ ቦታ የስንካርብ አጠገብ በመባል ይታወቃል ቦዔር አራት መቶ አርባ አንድ ዓመት ከኖረ በኋላ ሞተ ልጁ ፋሌቅም (የመልካጼዴቅ አባት) ራሱ ቦኤሪ ባሾነባት መቃብር ቀበረው ቦታዋም በስሙ ተሰየመች፡፡

135. ፋሌቅ አራት መቶ ሰላሳ ዓመት ኑሮ ሞተ ልጁ ራግውም ገነዘው ቀበረውም ራግው ሁለት መቶ ሠላሳ ዓመት ሲሆነው የሴም የካምና የያፌት ልጆች ተሰበሰቡ ከፍተኛ ወደሆነችውም ቦታ አንድ ላይ በመሆን ጉዞአቸውን ቀጠሉ የተጓዙበት ቦታ ንስቆባቁእ ይባላል፡፡

136. በዚሁም ይኖሩ ጀመር በሱሩያን በዕርዕና በከላዳውያንም ቋንቋ ይናገሩ ነበር፡፡ የአዳም የንግግር ቋንቋ የእብራውያን ቋንቋ ነበር የሚሉ ሁሉ ውሸታሞች ናቸው፡፡

137. በእግዚአብሔር ቀኝ የሚቆሙ ሁሉ በሱርስት ቋንቋ ብቻ ይናገሩ ነበር፡፡

# ምዕራፍ ፬ ዝርወት

ወበህየ ዘበመዋዕሊሁ ለራግው ሐነው ማሕፈደ በባቢሎን ተፋለጡ ዘዘዚአሆሙ ልሣናቲሆሙ።

1. ወሶበ ርእየ ራግው ከመተፈልጡ አሕዛብ እስከአፅናፈ ዓለም በህየ ሐዘነ ወሶበኮኖ ለራግው ፪፻፴ወ፱ ዓመት ሞተ።
2. ወገነዞ ወልዱ ሴሮሕ ወቀበሮ ውስተሀገር ወሰመያ በስመዚአሁ።
3. ወእምዝ ተፈልጡ ሕዝብ ወኮኑ ዘዘዚአሆሙ ወተካፈልዋ ለምድር ወኮኑ ለደቂቀሴም ፴ወ፭ ነገሥታት ወለደቂቀካም ፴ወ፭ ነገሥት ወለደቂቀያፌት ፴ወ፯ ነገሥት።
4. ወኮነ መንግሥቶሙ ለደቂቀ ሴም እምወሰነምድረ ፋርስ መንገለ ምስራቅ እስከባሕር ሆድስፌን ዘመንገለምሥራቅ።
5. ወመንግሥቶሙ ለውሉደያፌት እምወሰነ ደብር ቅዱስ ወደብረኑን ዘመንገለምሥራቅ እስከ ባሕረገባዖን ወእምባሐረ ምፅጣሮስ እስከ ዓቢይ ባሕር።
6. ወአዲ በሙ ሲመት በውስተምድር ወሶበኮኖ ለሴሮን ፻፴ወ፱ ዓመት ነገሠ ናምሩድ ሐያል ውስተኩሉ ምድር ወኮነ መንግሥቱ ቀዳሚ እምባቢሎን።

# ምዕራፍ ፬ ዝርወት

በዘመነ ራግው ሰዎች በባቢሎን ግንብን ሠሩ ከዚህ ጊዜ ጀምሮም የየራሳቸው ቋንቋ ሲኖራቸው ስለቻለ ሰዎች ተለያዩ።

1. ራግው አሕዛብ በቋንቋ እንደተለያዩ ባየ ጊዜ አዘነ ራግው በሁለት መቶ ሠላሳ ዘጠኝ ዓመቱ ሞተ።
2. ልጁ ሴሮን ገነዘው ባገሩም ቀበረው የቀበረበትንም ቦታ በስሙ ሰየመው።
3. ከዚህ ጊዜ ጀምሮ ሕዝቦች ተለያዩ ምድርንም ተካፈሉዋት ለሴም ልጆች ሰላሳአምስት ነገሥታት ለካም ልጆች ሰላሳአምስት ነገሥታ ለያፌት ልጆች ሰላሳ ሰባት ነገሥታት ሆኑላቸው።
4. የሴም ልጆች መንግሥት ከፋርስ ምድር ጀምሮ ወደምስራቅ ይደርሳል ይህንንም ሆድስፌን የሚባለውን የምስራቁን ባሕር ይይዛል።
5. የያፌት ልጆች መንግሥት ከደብርቅዱስ ዳርቻ ተነስቶ "ደብረኑን" ወደተባለው ቦታና ወደምሥራቅ አቅጣጫ አስከሚገኘው ምፅጣሮስ ወደሚባለው ቦታ መሄጃ ይደርሳል።
6. ሁለተኛውም ግዛት በምድር ላይ ነበራቸው ሴሮን መቶ ሰላሳ ዘጠኝ ዓመት ሲሞላው ሐይለኛው ናምሩድ ነገሠ ብዙ አገሮችንም ተቈጣጠረ ለመጀመርያ ጊዜ የነገሠው ግን በባቢሎን ነው።

7. ወውእቱ ዘርእየ ውስተ ሰማይ ፀሊመ ስጠተ ወሐመልሚለ አክሊለ።

8. ወአዘዘ ለሱስን ምስለ ከመይግበር ሎቱ ወአክሊለ ዘከመርእየ ውእቱኒ ገብረ ሎቱ አክሊለ እምያክንት ወበሰንፔር ወበመረግድ ወአስተቀፀሎ ዲበርእሱ።

9. ወውእቱ ቀዳሚ ዘገብረ አክሊለ ወበእንቲአሁ ይቤ ዘአልቦ አእምሮ ከመወረደ ሎቱ አክሊል እምሰማይ ወኮነ መንግሥቱ ፷ ወ፱ ዓመተ ወሞተ።

10. ወኮነ መንግሥቱ ለሴሩን ፻ ወ፴ ዓመት እምአዳም ወዲበመዋዕሊሁ ለሴሩሕ ሴሙ ላእሌሁ ሰብአግብፅ ንጉሠ ዘስሙ ፍርቆር።

11. ወነግሠ ላእሌሆሙ ፷ ወ፰ተ ዓመተ ወበመዋዕሊሁ ነግሠ ላእለሱባ ንጉሥ ዘስሙ ፊርኖስ ወአስተጋብአ ኀበመንግሥቱ ፪ተ ዓበይተሀገር አውቂና ወልያ።

12. ወሐነፀ በ፪ሆን አህጉር ጥቅመ ዘወርቅ ወእምድህሬሁ ነግሠ ዘስሙ ናክቶል።

7. ናምሩድ ጥቁር የተቀደደ የሚመስል ምልክትንና የተለያየ የቀለም መልክ ያለውን አክሊል በሰማይ ላይ አይቷል።

8. ናምሩድ ሱስን የተባለውን ሰው ከሰማይ ላይ ባየው መሠረት አክሊል እንዲሠራለት አዘዘው። እሱም ከተለያዩ የዓልማዝ፣ የዕንቁና የወርቅ ንጥረነገሮች አክሊልን ሠርቶ በራሱ ላይ ደፋለት።

9. ንጉሥ ሁኖ በራሱ ላይ አክሊልን በመድፋት ናምሩድ የመጀመርያ ነው ነገር ግን ናምሩድ ከሰማይ አክሊል እንደወረደለት የሚናገር መረዳት የተሳነው ልበቢስ ነው ተብሏል። የናምሩድ ዘመን ስድሳ ዘጠኝ ነው ከዚያ ሞተ።

10. ከናምሩድ በፊት የነገሠው ሴሩን ከአዳም በኋላ መቶ ሰላሳኛ ሁኖ ነግርሷል። ሴሩህ ግብፅንም ጠቅልሎ ሲገዛ ግብፃውያን ዓምፀው ለራሳቸው ለመጀመርያ ጊዜ ፍርቆር የተሳለውን ንጉሥ አነገሱ።

11. ፍርቆር በግብፃውያን ላይ ስድሳ ስምንት ዓመት ነገሰ ፊርኖስ የተባለውም ንጉሥ ሱባ በተባለው አገር በነገሰ ጊዜ ሁለት ያገር ታላላቅ ሰዎችን ጠራ። እነዚህን ሰዎች አውቂርና ካልያ ከተባለው አገር ነው የጠራቸው።

12. በነዚሁ ሁለት አገሮች በወርቅ የተለበጠ ግንብን ይህ ንጉሥ መሥራቱ ይነገራል። ከሱ ቀጥሎ ናቶል የተባለው ንጉሥ ነገሠ።

13. ወሐነፀ ጥቅመ ሱባ ወኮነት ሱባ ዘይነግሣ ላእሌሃ አንስት እስከመዋዕሊሁ ለሰሎሞን ወልደዳዊት፡፡

14. ወበመዋዕሌሁ ለሴሩን አምለኩ ሰብእ ጣዖታተ ወሰገዱ ሎሙ ወሐደግዎ ለእግዚአብሔር ወተፈልጡ ዘዘኢአሆሙ ውስተምድር እንዘአልቦሙ መምህር ወኢገባሬ ህግ ወሥርዓት ወዘይመርህ ውስተፍኖተርትዕ አበሱ ወክሕዱ ወሐደግዎ ለእግዚአብሔር፡፡

15. ወኮነ ዘዘኢአሆሙ እስመቦ እምኔሆሙ ዘያመልኮሙ ለፀሐይ ወለወርኅ ወቦ እምኔሆሙ ዘያመልኮ ለሰማይ ቦ እምኔሆሙ ዘያመልኮ ለጣዖት ወቦ እምኔሆሙ ዘያመልኮሙ ለከዋክብት ቦ እምኔሆሙ ዘያመልካ ለምድር ወቦ እምኔሆሙ ዘያመልኮሙ ለእንስሳ ወቦ እምኔሆሙ ዘያመልኮሙ ለዕፀው ወቦ እምኔሆሙ ዘያመልኮሙ ለማያት ወለነፋሳት እስመአጋንንት ዓየሩ አዕይንተ ሆሙ፡፡

16. ወረሰዩዎሙ ውስተፅልመት እንተ አልባቲ ብርሃን ወአልቦ እምውስቴቶሙ ወኢመኑሂ ዘየአምን ትንሣኤ ሙታን በእለተፍዳ አላ ባህቱ ሶበ ይመውት ፩ እምኔሆሙ ይገብሩ አዝማዲሆሙ ሥእለዚአሆሙ ወኢይትመተር ተገዘካሩ፡፡

13. ሱባ በተባለችውም አገር ግንብን ገነባ፡፡ በዚችው አገር እስከ መዋዕለ ሰሎሞን ወልደዳዊት ድረስ ሴቶች ብቻ እየነገሱ ኖሩ፡፡

14. ሰዎች ጣዖትን ማምለክና እግዚአብሔርን መካድ ጀመሩ ለጣዖቶች ሠገዱ በዚህም የርስበርስ መለያየት እየሰፋ ሄደ ይህ ሁሉ ሲሆን ግን ተው ተመለሱ የሚላቸው አስተማሪ ፈፅሞ በዚህ ምድር አልነበረም፡፡

15. የየግላቸውንም መንገድ ተከተሉ ፀሐይን ያመለከ አለ ጨረቃንም ያመለከ አለ ሰማይን ያመለከ አለ ጣዖትን ያመለከ አለ ኮከቦችን ያመለከ አለ ምድርን ያመለከ አለ እንስሳትን ያመለከ አለ ዕንጨቶችን ያመለከ አለ ውሆችንና ነፋሶችን ያመለከ አለ ሰዎች ይህን ሁሉ ለማምለክና ከእግዚአብሔር ለመራቅ የቻሉት በአጋንንት ስለታወሩ ነው፡፡

16. ሠይጣኑም መጨረሻ ወደሌለው የጨለማ ዐዘቅት ከተታቸው ከነሱ መካከልም ማንም በዘመን መጨረሻ የሙታን ትንሣኤ እንዳለ ፈፅመው አያምኑም ነበር የሞተውን ሰው ሥእል ሥለው ለመታሰብያነት ያስቀምጡ ነበር፡፡

17. ወመልአ ኵሉ ምድረ ኃጢአት ወመልአ ሥእለእድ ዘግቡር በእደሰብእ ወሶበኮና ለሴሩኅ ፪፻፴ ወ፯ ዓመት ሞተ ወገነዞ ናኮር ወልዱ ወቀበሮ ውስተ ሀገር ዘሐነፀ ለሊሁ ወሰመያ በስመዚአሁ።

18. ወሶበኮና ለናኮር ፷ወ፰ ዓመት ርእዮሙ ልዑል እግዚአብሔር ለኵሉ ፍጥረት እንዘይሰግዱ ለአማልክት ወማሰኑ በዕልወት ወፈነወ ላዕሌሆሙ ዓቢይ ድልቅልቅ ወተሰጥሙ ኵሎሙ አማልክቲሆሙ ውስተምድር።

19. ወእሙንቱ ኢተመይጡ እምጌጋዮሙ ወኢእምእከዮሙ ወአዲ ወሰኩ ገቢረአበሳ ወሐጢአት ወእም ፻ ወ፳ ዓመት ምኩናኑ ለታራ ዘነበረ ሥራየ ወቀዳሚ ነገሩ እስመብእሲ ባዕል ሞተ ወገብረ ወልዱ ሥእለአቡሁ ዘወርቅ ወአንበሮ ዲበመቃብሪሁ በከመሥርዓቶሙ ዘገብሩ ላእሌሁ በእማንቱ መዋዕል።

20. ወሐደገ ብእሴ ዘየዓቅቦ ወቦአ ሠይጣን ላእለውእቱ ሥዕለወርቅ ወተናገሮ ለዓቃቢ በልሳነመዋቲ ወሖረ ወነገሮ ለወልዱ እምሃበውእቱ ሥእል ዘሰምዓ።

21. ወእምድሕረ ሕዳጥ መዋዕል ቦኡ ፈያት ውስተቤተ

17. ምድር በመላ በሐጢአት ተመላች የሰው የእጅ ሥእልም በየቦታው መላ ሴሩኅ ሁለት መቶ ሰላሳ ሰባት ዓመት ሲሞላው ሞተ ልጁ ናኮሪም ገነዘው ራሱ በሠራት ቦታም ቀበረው በስሙም ሰየማት።

18. የናኮር ዕድሜ ስድሳስምንት ዓመት ሲሆን ልዑል እግዚአብሔር ፍጥረትን ሁሉ ተመለከተው ጣዖትን ማምለክ ሥራው አድርጎ ነበርና ምድርን አነዋወጣትና በየቦታው ተክለው ያመልኩባቸው የነበሩት ጣዖታት ሁሉ ሠጠሙ።

19. እነሱ ግን ይህን ሁሉ የእግዙአብሔር ቁጣ ቢያዩም ከበደላቸውና ከክፋታቸው ጨርሰው ሊመለሱ አልቻሉም ታራ መቶ ሃያ ዓመት በገገርነት ሲኖር የሥራይን ነገር አስፋፋ በዘመኑ አንድ ሀብታም ሰው ሞተና የሐብታሙ ሰው ልጅ የሟቹን ምሥል ከወርቅ አስቀርፆ በመቃብሩ ላይ አኖረ። ይህ ከሱ በፊት ተለምዶ በቆየው ባህልና ሥርዓት አደረገው እኔ እበልጥ እኔ እበልጥ በመባባል የሟቹን ሥእል በመቃብር ላይ የማስቀመጡ ባህል እጅግ ተንሠራርቶ ነበር።

20. ይህ የሀብታሙ መዋች ልጅ ባባቱ መቃብር ላይ ላስቀመጠው የወርቅ ምስል ጠባቂ ሰው አስቀመጠለት በወርቅ ምስሉ ላይ ያደረው ሠይጣን ጠባቂውን ሰው በሟቹ ሰው አንደበት አነጋገረው ሰውየውም የሰማውን ለሐብታሙ ልጅ ነገረው።

21. ከጥቂት ጊዜ በኋላ ሽፍቶች የሟቹን ሃብታም ሰው ልጅ ቤት

መዋቲ ወነሥኡ ንዋየወልዱ ወሖረ ወልዱ ኀበመቃብረ አቡሁ አውየወ ወበከየ ዓቢየ ብካየ ወተናገሮ ሠይጣን እምውእቱ ምሥለወርቅ።

22. ወይቤሎ በከመቃለአቡሁ ኢትሕዝን ወኢትብኪ ኦ ወልድየ ሑር ወአምፅእ ወልደከ ወሡእ ሲተ ወትረክብ ኩሎ ንዋየከ ወሖረ ፍጡነ ወአምፅአ ወልዶ ዘይንእስ ወሦዖ ለሠይጣን።

23. ወቦአ ሠይጣን ላእሌሁ ወመሃሮሥራየማሪ ወኩሎ ግብረጣዖት ወእምአሜሃ ተምህሩ ሰብእ ይሡኡ ውሉዶሙ ለአጋንንት ወበተፍፃሜተ መዋዕለሕይወቱ ለናኮር ርእዮሙ እግዚአብሔር ልዑል ፍናሆሙ ለአጋንንት ወጌጋዮሙ ለሰብእ ወእከዮሙ ወዘከመይሰውኡ ውሉዶሙ ለአጋንንት ወይሰግዱ ለአማልክት።

24. ወፈነወ ላእሌሆሙ ዓቢይ ነፋስ ወገፍትዓ አማልክቲሆሙ ወደፈኖሙ ውስተምድር ወረሰየ መልዕልቴሆሙ አድባረ ዓበይተ እምንቱኒ ይነብሩ መትሕተአድባር እስከዮም።

25. ወበእንተዝ ይቤሉ ካልአን መፅአ በመዋዕሊሁ ለታራ አይገ ዘነፋስ ወአዲ ይቤሉ መምህራን ዘሕንደኬ

ዘረፉ ይህም ልጅ ወዳባቱ መቃብር ቤት መጥቶ ከወርቅ ምስሉ ፊት አለቀሰ በምስሉ ላይ ያደረው ሠይጣንም አናገረው።

22. ባባቱ እንደበትም ካናገረው በኋላ ገንዘቡ በሙሉ ሊመለስለት ከፈለገ ልጁን እንዲሠዋለት ጠየቀው። እሱም ትንሹን ልጁ አምጥቶ አርዶ ለሠይጣኑ ሠዋው።

23. ሠይጣን በዚሁ ሰው ከዚሁ ጊዜ ጀምሮ ገባበት የጥንቈላንም ሥራ አስተማረው የጣዖትንም ሥራ ሁሉ እንዲሠራ አደረገው። ከዚህ ጊዜ ጀምሮ ሰዎች ከዚሁ ሰው ልጆቻቸውን ለአጋንንት እያረዱ መሥዋዕት ማቅረቡን ተያያዙት የናኮር ዘመን ሲያልቅ ሲቃረብ የአጋንንትን ተንኰልና የሰዎቹን በአጋንንት መመራት እግዚአብሔር ተመለከተ ጣዖት አምላኪነታቸውንና ልጆቻቸውን ማረዳቸውንም አየ።

24. እግዚአብሔር ከፍተኛ ነፋስ ዓውሎ በነሱ ላይ ላከ አማልክቶቻቸውንም ገለባበጠ እነሱንም ወደምድር አስገብቶ ደፈናቸው ከበላያቸውም ተራራዎችን ሠራ። እነሱም ከነዚሁም እስከዘለዓለሙ በነዚህ ተራራዎች እንደተደፈኑ ይኖራሉ።

25. ሌሎች ደግሞ በታራ ዘመን የጥፋት ነፋስ ተነስቶ እንደነበር ይገልፃሉ እንዲሁም የሕንድ መምህራን ተራሮችና ኩረብቶች

ከመእሙንቱ አድባር ወአውግር ተፈጥሩ በመዋዕለ አይሕ በእንተ አምልኮ ጣዖት በእንተ ኃጢአቶሙ ለውሉደ ቃየል በውስተምድር።

26. በእንተዝንቱ ናሁ ሐሰወ ዘይቤ ከመእሉንቱ አድባር ወአውግር ተፈጥሩ እምጥንት ዘለዓለም።

27. **ወባሕቱ** ተፈጥሩ ሶበተምዖሙ እግዚአብሔር **በእንተዘአምለኩ** ጣዖተ ወሰገዱ ሎሙ ወኩሉ አድባር **ወአውግር** ዘውስተምድር ህለወ ውስቴሆን ሠይጣን ወጣዖት ወበመዋዕሊሁ ለናምሩድ ሐያል ሰገደ **ናምሩድ** ወአንበራ ውስተመካን ዘርእያ ለእሳት ተዓርግ **እምድር** እስከሰማይ ወሰገደ ለእሳት ዘርእያ ከመይትቀነይ ላቲ ወይደይ ውስቴታ ዕጣነ ለዝሉፉ።

28. እምውእቱ ጊዜ ሰገዱ ሰብአ ሰገል ለእሳት ወሶበተዓርግ እምሰማይ አሐዙ ያምልክዋ ወአዲ ፩ ብእሲ መኰንን ዘስሙ ሳስ ወረደ ሃበመካን ዘብሔረ አድራገን ውስተነቅዓፈልፈ ለማይ ወቆመ ህየ ፀዓዳ ፈረስ ወኩሎሙ እለመፅኡ ይትሐፀቡ እምውስተነቅዓፈልፈል ይሰግዱ ለውእቱ ፈረስ።

በጥፋት ውሃ ዘመን እንደተፈጠሩ ሲገልፁ ሌሎች ደግሞ የቃየል ልጆች በዚችው ምድር ጣዖትን ከማምለክ ጀምሮ ብዙ ሐጢአት ስለሰሠሩ የጥፋት ውሃ ሆነ ተራሮችና ኮረብታዎች በዚሁ ሊፈጠሩ ችለዋል ይላሉ።

26. ይህን ሁሉ ስንመለከት ተራሮችና ኮረብቶች ከጥንት ጀምረው ተፈጥረዋል የሚለውን ሰው ትክክል እንዳልሆነ እንመለከታለን።

27. እነዚህ ተራራዎችና ኮረብታዎች የተፈጠሩት እግዚአብሐር የሰውን ልጆች ስለተቈጣቸው ሊፈጠሩ ብቻ ችለዋል እግዚአብሐር ሰዎች ጣዖትን በማምለካቸው ምክንያት በቁጣ ስለፈጠራቸው በውስጣቸው አጋንንት አሉባቸው ይላሉ ናምሩድ በዘመኑ ከሰማይ እሳት አይቶ **ነበር**። ይህንንም ያየውን እሳት ያመልከው ጀመር። **ይህን ከሰማይ** እሳት ሊወጣ ያየበትን ቦታ ላየው እሳትን የሚሰግድበትና የሚያመልክበት አደረገው መላ ሕይወቱንም ለዚሁ ዕጣንን እያጤሰ ማምለኩን ቀጠለበት።

28. ሰብአሰገል ከዚሁ ጀምሮ ለእሳት መስገድ ጀመሩ። እሳቷ ወደሰማይ ስታርግ ደግሞ ያመልኩዋት ጀመር ዳግመኛም አንድ መኰንን ሳስ የሚባል ወደዚሁ ቦታ ውሃ (የሚመነጭበት) ወርዶ ቆመ ነጭፈረስንም በዚሁ አቆመ። ውሃውን ለመጠመቅ የሚመጡ ሁሉ ለዚሁ ለቆመው ፈረስ ይሠግዱ ጀመር እሱንም አመለኩት።

29. ወበእንተዝ ያዓብዩዎ ሰብአሰገል ወያከብርዎ ለውእቱ ፈረስ ወቦ እምኔሆሙ ዘይሰግዱ ሎቱ እስከዮም፡፡

30. በቀዳሚ ሶበ ሖረ ናምሩድ እምሐገር ለሐገር ቦአ ሐገረ ጥራውስ ወበህየ ረከቦ ለቦኒጦር ወልደኖኅ ዘራብዕ ትውልድ፡፡

31. ወርእዮ ናምሩድ ሰገደ ሎቱ ወይቤሎ ለምንት እንከ ትሰግድ ሊተ ወይቤሎ ለቦኒጦር መጻእኩ ኀቤከ ወነበረ ናምሩድ ፲ ዓመተ ከመይትመሐር ጥበበ ወምክረ፡፡

32. ወእምዝ እንዘያስተፋንዎ በኒጦር ይቤሎ ለናምሩድ ዳግመ ኢትምጻእ ኀቤየ ወሐሊፎ ናምሩድ መንገለምሥራቅ አጽሐፈ መጻሕፍተ በእንተኩሉ ዘመሐሮ በኒጦር ወልደ ኖኅ፡፡

33. ወሀሎ ህየ ብእሲ ዘስሙ አዝዱሴር ዘይት ቀነይ ለእሳት ወሶበርእየ ጥበቢሁ ለናምሩድ ወዘተምህረ ከዋክብተ ቀንዓ ላእሌሁ፡፡

34. ወሖረ ሠይጣን ዘያስተርኢ ኀበ እሳት ሥዓለ ወአስተብቁአ ኀቤሁ ከመይምሀሮ ጥበቢሁ ለናምሩድ ወአውሥአ ሠይጣን ወይቤሎ ለእመፈቀድከ እምሐርከ ፈፅም ሊተ ኩሎ ሕግየ ወሥርዓትየ ወስክብ ምስለእምከ ወአሐቲከ ወአዋልዲከ፡፡

29. ከዚያ በፊት ባዩት መሠረትም ሰብአሰገል ፈረሱን ከፍ ከፍ ያደርጉት ነበር፡፡ ከነሱም አብዛኞቹ ወደሱ ይሰግዱ ነበር፡፡

30. ናምሩድ ካገር አገር ከቦታ ቦታን መጐብኘት ባደረገ ጊዜ ከኖኅ አራተኛ ትውልድ የሆነውን ቦኒጦር አገኘው፡፡

31. ናምሩድ የኖኅ የልጅ ልጅ የሆነውን ቦኒጦር ባየው ጊዜ ሰገደለት በዚህ ጊዜ ለምን ወደኔ ትሰግዳለህ አለው በብዙ ድካም ስላገኘሁህ ሰገድኩልህ አለው ከሱም ዘንድ ናምሩድ ጥበብንና ምክርን ለመማር ፲ ዓመት ኖረ፡፡

32. ከአሥር ዓመት በኋላ የኖኅ አራተኛ ትውልድ የሆነው በኒጦር ናምሩድን ሸኘው ድጋሚም ወደሱ እንዳይመለስ ነገረው ናምሩድ ባለበት ከወደ ምሥራቅ ተጉዞ ከቦኒጦር የተማረውን ሁሉ በመጻሕፍት አፃፈው፡፡

33. በዚሁ አገር አዝዱሴር የተባለ ሰው ነበረ ሰውየው ለእሳት ይገዛ ነበር የናምሩድን ትምህርትና ዕውቀት አይቶ በናምሩድ ላይ ቀናበት፡፡

34. በእሳት እየተመሰለ ሲታይ የቆየው ሠይጣን ወደአዝዱሴር ሄደና አዝዱሴርም የናምሩድ ጥበብ እንዲያስተምረው ሠይጣኑን ጠየቀው ሠይጣኑ በዚህ ጊዜ የናምሩድን ጥበብ እንዳስተምርህ ከፈለግህ ሥርዓቴንና ህጌን ፈፅም ከናትህ እህቶችህና ሴት ልጆችህ ጋር ሥጋዊ ግንኙነትን ፈፅም

35. ወገብረ አዝጼሴር ኩሎ ዘአዘዞ ሠይጣን እምይእቲ እለት አሐዙ ሰብእ ይስክቡ ምስለእምሙ ወአዋልዲሆሙ ወአሐቲሆሙ።
36. ወመሀሮ ሠይጣን ለአዝጼሴር ኩሎ ትምህርተ ሥራይ ወማርያን ወትምህርተ ጣዖት ወፀነዐ በዛቲ ትምህርት ሰብእ ከለዳውያን ወኩሉ ዘተምሀረ ዘንተትምህርተ አልቦቱ ሥርየት እምኀበ እግዚአብሔር።
37. ትምህርትሰ ዘተምሀረናምሩድ እምኀበ ቦኒጦር ወልደኖኅ እምእግዚአብሔር እስመትምህርተ ከዋክብት ውእቱ ለአእምሮ ዓመታት ወአውራሕ ውእቱ ወሰብአፅርዕ ይሰምይዎ ለዝንቱ ትምህርት አስጠሮንያ።
38. ወሐነፀ ናምሩድ ዓበይተ አሕጉረ ወለእሉ አህጉር ከመዝ አስማቲሆሙ ግደብሮር ወእለርእሱ ወሰልው ወቀጦአስትኑን ወአርዳጊን ወአሕጉረ እድርገን ወለሳን።
39. ወካልአኒሂ አሕጉር ዘገብረ ለሊሁ ወሶበ ኮኖ ለታራ አቡሁ ለአብርሃም ፪፻፷ ወ፫ ዓመተ ምተ ወገነዞ ወልዱ አብርሃም ወቀበሮ ውስተሀገረታግራን።
40. ወእምዝ አዘዞ እግዚአብሐር ለአብርሃም ወቀበሮ ለአቡሁ ወአዘዞ ይሁር ውስተሀገር ቅድስት ተንሥአ ወነሥአ ብእሲቶ ሣራ ወለተ አቡሁ ወሆረ ውስተምድረአሞሬዎን

አለው።
35. አዝጼሴር ከሠይጣን የተማረውን ሁሉ ፈፀመ የሱንም ሠይጣናዊ ሥራ ተከትለው ሰዎች እናቶቻቸውን እህቶቻቸውንና ሴት ልጆቻቸውን ይገናኙ ነበር።
36. ሠይጣን ለአዝጼሴር የሥራይንና የጥንቈላን ትምህርት ሁሉ አስተማረው የከለዳውያን ሰዎች ሁሉ በዚሁ ትምህርት ተሠማሩ ይህንን ተግባር የሚከተል ሁሉ ከእግዚአብሐር ዘንድ ይቅርታ የለውም።
37. ከኖኅ አራተኛ ትውልድ ከሆነው ቦኒጦር ዘንድ ናምሩድ የተማረው የከዋክብት ትምህርት የዓመታትንና የወራትን መለዋወጥ ለማወቅ የሚረዳን ነው ይህን ትምህርት ፅርዓውያን አስጠሮንያ እያሉ ይጠቅሱታል።
38. ናምሩድ ትልልቅ አገሮችን ሠራ የነዚህም አገሮች ስም ግደብሮር አለር እሱ፣ ስልው ወቀጦአስትኑን፣ አርዳጊን የእርድገንንና የወለሳን አገሮች ናቸው።
39. ሌሎችንም አገሮች ሠርቷል ታራ ሁለት መቶ ስድሳ ሦስት ዓመት ሲሞላው ሞተ ልጁ አብርሃምም ገነዘው ታግራን በተባለው አገርም ቀበረው።
40. በዚህ ጊዜ እግዚአብሔር አብርሃምን አዘዘው አባቱን ይቀብር ዘንድ እሱም ቀበረው ወደተቀደሰችውም አገር ይሄድ ዘንድም አዘዘው አብርሃምም ሚስቱን ሣራንና የወንድሙን ልጅ ሎጥን

እንዘዓመታቲሁ ፰ወ ፳ቱ ክረምት ተቃተለ ምስለ አሕዛብ ወሰደዶሙ ወጕዩ እምቅድሜሁ፡፡

1. ወበውእቱ ጊዜ አልቦቱ ውሉድ እስመሣራ ብእሲቱ መካን ይእቲ ወሰበተመይጠ አብርሃም እምቅትለ አሕዛብ አዘዞ እግዚአብሐር ይሁር ኀበዋሪግናን ዘበትርጋሜሁ ደብረማኖስ ብሂል፡፡

2. ወሆረ አብርሃም ወሰበርእዮ ለመልከጼዴቅ ሰገደ ሎቱ ወአስተብረከ እስመበህየ ተራከበ ምስለ መልከጼዴቅ ካህኑ ለእግዙአብሔር ልዑል፡፡

43. ወሰበርእዮ አቅረበ ቅድሜሁ ሕብስተስንዳሌ ንፁሐ ወወይነ ፅሩየ ወባረኮ መልከዜዴቅ ወአስተብቁአ በእንቲአሁ፡፡ ወውእተ ጊዜ አዘዞ እግዚአብሔር ለመልከዜዴቅ ከመይትላፀይ ርእሶ ወይምትር ፅፍሮ ወያሠኒ ተግባሮ ወገብረ ከማሁ፡፡

44. ወእምዝ ቀደሰ መልከዜዴቅ ቁርባነ ወአቅረበ ለአብርሃም እምውእቱ ሕብስት ወወይን ወወሀበ አብርሃም ለመልከዜዴቅ አሥራተ እምኩሉ ንዋዩ፡፡

45. ወካዕበ ተናገሮ እግዚአብሔር ለአብርሃም ወይቤሎ ናሁ አዓብየከ ወአከብረከ እስመዓፀይንትየ ኀቤከ እስመተወከፍከ በረከተ መልከዜዴቅ ወኮንከ ድልወ ትቁረብ እምእደዊሁ ለመልከዜዴቅ፡፡

ይዞ በ75 ዓመቱ ተነሳ ከአሕዛብ ነገሥታት ጋርም ጦርነት ገጠመ እነሱም ከፊቱ ሸሹ፡፡

41. በዚሁ ጊዜ ለአብርሃም ልጅ አልነበረውም ሚስቱ ሣራ መካን ነበረችና አብርሃም ከጦርነት ከተመለሰ በኋላ እግዚአብሔር አብርሃም ዋሪግናን ወደተባለችው ቦታ ይሄድ ዘንድ አዘዘው ዋሪግናን ማለት ደብረዋኖስ ማለት ነው፡፡

42. አብርሃም ጉዞውን ቀጠለ መልከጼዴቅን ባየ ጊዜ ወደምድር ሰገደ የእግዚአብሔር ካህን የሆነውን መልከጼዴቅ ተገናኝቶታል፡፡

43. አብርሃም መልከዜዴቅን ባየው ጊዜ ከሱፊት የስንዴ ሕብስትና የተጣራ የወይን ጭማቂ አቀረበለት በዚህ ጊዜ መልከጼዴቅ አብርሃምን ባረከው ስለሱም ወደእግዚአብሔር ማለደ፡፡ በዚህ ጊዜ እግዚአብሔር ጠጉሩን እንዲላጭ ጥፍሩንም እንዲቆርጥ ለመልከጼዴቅ ነገረው፡፡ እሱም የታዘዘውን አደረገ፡፡

44. መልከጼዴቅ በዚህ ጊዜ ቀደሰና ለአብርሃም ከሕብስቱና ከወይኑ አቁረበው አብርሃም በበኩሉ ለመልከጼዴቅ ካለው ሀብት ሁሉ አንድ አሥረኛውን ሠጠው፡፡

45. እግዚአብሔር በድጋሚ ለአብርሃም ተናገረው እንዲህም አለው "የመልከዜዴቅን በረከት ተቀብለህ በመልከጼዴቅ እጅ ቁርበሃልና እኔ አንተን ከፍ ከፍ አደርግሃለሁ አከብርህማለሁ ዓይኖቼም ካንተ ላይ ናቸው"፡፡

5. ወፌድፋደ እባርከከ ወአበዝሕ ዘርእከ።

## ምዕራፍ ፭ ሁረተ አብርሃም ወደቂቁ

1. ወሶበኮና ለአብርሃም ፹ወ፮ ዓመተ ወለደ ለእስማኤል እምአጋር ግብፃዊት ዓመት እንተወሀባ ፈርኦን ንጉሠግብፅ ለሣራ ብእሲተ አብርሃም እስመ ሣራሰ እኅቱ ለአብርሃም እምአቡሁ ወኢኮነት እምእሙ።

2. እስመታራ አውሰበ ፪ አንስተ ለእሐቲ ስማ ቱና እምኔሃ ተወልደ አብረሃም ወሞተት ወእምድሕሬሃ አውሰበ እንተስማ ትሕዴፍ ወይእቲ ወለደታ ለሣራ

3. ወበእንተዝ ይቤሎ አብርሃም ለንጉሠ ግብፅ ሣራ እሕትየ ይእቲ።

4. ወሶበኮና ፻ወ፱ ዓመተ ወረደ እግዚአብሔር ወወሀባ ለሣራ ወልደ ወእምአሜሃ ኮና ፻ዓመት ወወለደቶ ሣራ ለወልዳ ይስሐቅ ዘወሀቦ እግዚአብሔር ለአብርሃም።

5. ወሶበኮና ለይስሐቅ ፲ወ፪ ክረምት ፈቀደ አብረሃም ይሡዖ ለይስሐቅ በደብረማኖስ መካነ ዘተሰቅለ ቦቱ እግዚእነ

46. እግዚአብሐር እንደገና ለአብርሃም እንዲህ አለው "ከፍ አድርጌ እባርክሃለሁ ዘርህንም አበዛለሁ።

## ምዕራፍ አምስት የአብርሃምና የልጆቹ ሒደት

1. አብርሃም የሰማንያ ሰባት ዓመት ሰው ሲሆን እስማኤልን ከአጋር ግብፃዊት ወለደው። አጋር አብርሃም ወደግብፅ በተሰደደ ጊዜ የግብፅ ንጉሥ ፈርኦን አገልጋይዋ ትሆን ዘንድ አጋርን ለሣራ ሠጥቶአታል ሳራ የአብረሃም እሕትነቷ በናት አይደለም ባባት ብቻ የአብርሃም እህት ናት።

2. ታራ ሁለት ሚስቶችን አግብቷል የመጀመርያዋ ሚስቱ ቱና ትባላላች ከሷ አብርሃም ተወለደ። ቱና አብርሃምን ብቻ ወልዳ ሞተች። ታራ እንደገና ትሕዴፍ የምትባለውን ሁለተኛዋ ሚስት አገባ። ከሷ ሣራ ተወለደች።

3. አብርሃም ለግብፁ ንጉሥ "ሣራ እሕቴ ናት" ሲል የቻለው በዚሁ ምክንያት ነው።

4. አብረሃም የዘጠና ዘጠኝ ዓመት ሰው ሲሆን እግዚአብሔር ወርዶ ለሣራ ልጅ ሠጣት አብርሃም መቶ ዓመት ሲሞላው ሣራ ልጇ ይስሐቅን ወለደችው እሱን እግዙአብሔር ለአብርሃም ሠጥቶታልና።

5. ይስሐቅ የአሥራ ሁለት ዓመት ልጅ ሲሆን አብርሃም ከእግዚአብሔር በታዘዘው መሠረት ደብረማኖስ በተባለው ቦታ

ወአምላክነ ወመድኀኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወስመ ለውእቱ መካን ጎልጎታ ወበሕየ ፈጠሮ እግዚአብሐር ለአዳም።

6. ወአዲ በህየ ርእየ አብረሃም በግዓ እሱረ ውስተዕፀ ወበህየ ተቀብረ ሥጋሁ ለአቡነ አዳም ወበህየ ቦቱ ለመልከጼዴቅ ወበህየ ርእዮ ዳዊት ለመልአከእግዚአብሔር እንዘይፀውር መጥባሕተ አማስኖታ ለኢየሩሳሌም።

7. ወአዕረገ ለይስሐቅ ውዕተምሥዋእ አርአያሁ ለስቅለተ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ በእንተመድኀኒተ አቡነ አዳም ወውሉዱ እስመይቤ እግዚእነ ወአምላክነ ወመድኀኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ "አብርሃም አቡክሙ ተመነየ ይርአይ ዕለትየ ወርአየ።

8. ወበግዕ ዘርእየ አብርሃም እሡረ ዲበዕፀ ሕየንተ ይስሐቅ አምሳለስቅለቱ ለእግዜአነ ወአምላክነ ወመድኀኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ

9. ወበይእተ ሰዓት አእረገ አብርሃም ለይስሐቅ ከመይሡኦ ቀዳሚተ ሕንፀታ ለኢየሩሳለም እስመመልከጼዴቅ ካህኑ ለእግዚአብሔር ሶበተግህደ ሰብእናሁ ነገሥታተ ምድር ወአሕዛብ መፅኡ ሐቤሁ እምኩለሄ ከመይንስኡ በረከቶ

ሊሰዋው ወደደ። ደብረማኖስ የተባለው ቦታ በኋላ ጌታችን መድሐኒታችን ኢየሱስክርስቶስ ለሰው ልጆች ቤዛ ሆኖ የተሰቀለበት ጎልጎታ ነው። እግዚአብሔር አዳምን በጎልጎታ ነው የፈጠረው።

6. እንደገናም አብርሃም በዚሁ ቦታ በእንጨት ላይ የታሰረን በግ አይቷል በዚሁ ቦታ የአባታችን አዳም ሥጋ ተቀብሯል በዚሁ ቦታ ዳዊት የኢየሩሳሌምን የጥፋት ሠይፍ የያዘ የእግዚያብሔርን መልአክ አይቷል

7. አብርሃም ይስሐቅን ወደ መሠዊያው የቀረበበት ምክንያት የጌታችን መድሐኒታችን እየሱስ ክርስቶስ ስለ አዳምና ልጆቹ ድሕነት የሚሰቀለውን ስቅለት አርአናያ ነው ጌታችን እየሱስ ክርስቶስ አብርሃም አባታችሁ ዕለቴን ያይ ዘንድ ተመኘ አየም በማለት የገለፀው የዚህን ምሥጢር ሲገልፅ ነው።

8. በዕንጨት ላይ ታሥሮ አብርሃም ያየውንም በግ የጌታችን መድሐኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ምሳሌ ነው።

9. አብርሃም ይስሐቅን ሊሰዋው ዘንድ ወደተራራ ያወጣበት ምክንያት የኢየሩሳሌም የመታደስ ወቅት ስለነበር ነው መልከጼዴቅ የእግ ዚአብሔር ካህኑ በተገለጠ ጊዜ አሕዛብ ከያቅጣጫው በረከቱን ለመቀበል ወደሱ ጐረፉ።

10. ወእሉ እሙንቱ እለመጽኡ ሀቤሁ ነገሥት አጕተማልንግ ንጉሠ እለግንደርዋ ዘመት ሕቴሁ ለንጉሠ ሳኤል ወባርግ ንጉሠ ዳላዘር ወከርጉን ንጉሠ እልሞ ወባርኤል ንጉሠ ኢማኢሙራ ወበርኤልንጉሠ ሰዶም ወበሪኡ ንጉሠ አግያት ወሲመን ንጉሠ አሞሌዎን ወሲይን ንጉሠ አሞለዎን ወሲላይን ንጉሠ ዳም ወሐናን ንጉሠ ደማስቆ ወበጋጣር ንጉሠገዳም።

11. እነግረከ ኦ ወልድየ ቀሌሚንጦስ ሰበርእይዎ እሉ ነገሥት ለመልከጼዴቅ ንጉሠ ሰላም ወካህኑ ለእግዜአብሔር ወሶበሰምዑ ነገሮ አእበይዎ ወአክበርዎ ፈድፋደ ወሰአልዎ ከመይሁር ምስሌሆሙ ውስተበሐውርቲሆሙ።

12. ውእቶምኒ ነገሥት መጽኡ ኀበ ሐዋርያ እምውእቱ መካን ዘአዘዞ እግዜአብሔር ይንበር ውስቴቱ እሙንቱስ ነገሥት ተማከሩ በበይናቲሆሙ ከመይህንፁ በንዋዮሙ ቤተመቅደሰ ወሐነፁ ወወሀብዎ ሎቱ ውእቱኒ ሰመያ ኢየሩሳሌም።

10. የመልከጼዴቅን በረከት ያመጡት ነገስታት የእለግንደርዋ ንጉሥ አጕተማልንግ የሳኤል ንጉሥ የበታች የሆነ የዳላዘር ንጉሥ የእልሞ ንጉሥ የኢማኢሙራ ንጉሥ ባርኤል የሰዶም ንጉሥ የሆነው በርኡ የዓግያት ንጉሥ በሪኡስ የአለዎን ንጉሥ ሲይን የሰላም ንጉስ ሲልአደን የደማደስቆ ንጉሥ አላን የባዳም ንጉስ በጋጣሮ ናቸው።

11. ልጀ ቀሌሜንጦስ ሆይ የነገሥታቱን ሁናቴ እገልጽልሃለሁ እኒህ ከላይ ስማቸው የተዘረዘረው ነገስታት በየበኩላቸው ወደያገራቸው አብሮአቸው ይሄድ ዘንድ የእግዚአብሔር ካህንና የሰላም ንጉሥ የሆነውን መልከጸዴቅን ለመኑት ንግግሩን ሰምተው አክብረውታልምና።

12. መልከጼዴቅ ግን እግዚአብሔር በዚሁ ቦታ እንዲቀመጥ ስላዘዘው ለመሄድ እንደማይችል ነገራቸው ነገሥታቱ በዚህ ጊዜ ተመካከሩና ቤተመቅደስን በገንዘባቸው እንዲሰሩ ወስኑ መቅደስንም ሠርተው ለመልከጼዴቅ አስረከቡት መልከጼዴቅም መቅደሱን ኢየሩሳሌም አላት።

13. ወእምዝ መፅኡ እምልኡካነ ነገሥት ኀበ መልከጼዴቅ ወሰበርእዩዎ አክበርዎ ፋድፋደ ወወኀብዎ ብዙሐ አምሃ።

14. ወነበሩ ነገሥት እንዘየዓብይዎ ወያከብርዎ ወይሰምይዎ አበነገሥት ወበ ካልእን እለይቤልዎ ከመልከጼዴቅ ኢይመውት በእንተ ዘይቤ ዳዊት አንተ ካህኑ ለዓለም በከመሚመቱ ለመልከጼዴቅ ወዳዊት ኢይቤ ኢይመውት ወእፎ ኢይመውት እንዘተ ዝመደሰብእ ውእቱ እምትዝምደ ሰብእ ውእቱ።

15. አላ ባሐቱ እግዚአብሐር ልው ል አዕበዮ ወአክበሮ ወረሠዮ ካህኑ ወአዘከረ ሙሴ በውስተ ኦሪት ቀዳሚ መዋዕሊሁ ለመልከጼዴቅ ወልደፋሌቅ ወልደአርፋክስድ

16. ወበዓመታቲሁ ለአብርሃም ነግሠ ንጉሥ በምሥራቅ ዘስሙ ከርመስ ወወለደ ውሉደ ወሐነፀ አሕጉራተ ዓበይተ ወሰመዮሙ በስመውሉዱ ስመስጠ አመርያ ወቀሪን ወለዩሁ ወእምድሕረ ዓመት ሖረ መንግለ ደሴት መብራ ለለአሐዱ እምኔሆን ጥቅመ ወሰመዮን ለጥቅም

13. ከቴማን ነገሥታቸም አንድ መልእክተኛ ወደመልከዜጼቅ መጥቶ ባየው ጊዜ እጅግ አከበረው ብዙ እጅ መንሻንም ለመልከጼዴቅ ሠጠው።

14. ነገሥታት መልከጼዴቅን በከፍተኛ መዓርግ ይመለከቱት ነበር የነገሥታት አባት በማለትም ሰየሙት ብዙዎች መልከጼዴቅ አይሞትም የማለት አስተሳሰብ አድሮባቸው ነበር ነቢዩ ዳዊት አንተ እንደመልከጼዴቅ ሹመት የዓለም ካህን ነህ ያለውን በመመለከት ነው አይሞትምያሉት ዳዊት ግን አይሞትም አላለም እሱ ሰው ሆኖ ስለተፈጠረ እንዴት አይመትም ይላሉ።

15. ነገርግን እግዚአብሐር ልዑል ካህንም አደረገው ሙሴ የመልአዬዴቅን በእግዚአብሐር ከመመረጡ በፊት ያለውን ሕይወቱ በኦሪት ውስጥ አልመዘገበም ነገር ግን እሱ የአርፋክስድ ልጅ የፋሌቅ ልጅ መሆኑ ይታወቃል።

16. በዘመነ አብርሃም አንድ ንጉሥ በምሥራቅ ክፍል ነግሦ ነበር ስሙ ብርመስ ይባላል ብርመስ አራት ልጆችን ወልዷል አራት አገርንም አቅንቶ በአራቱ ልጆቹ ስም ሰጠ አመርያ ቀሪንና ለዩሁ ብሎ ሰየማቸው ከዛ ዓመት በኋላ ይህ ንጉስ ወደደሴት ሄደ በደሴቶቹም ግንቦች ሠርቶ አቆመና

በስመብእሲ·ቱ።

17. ወገብሩ ሰብአ ሀገር ሥእለዚአሁ ወሰገዱ ለቤ·ቱ ወሶበሞተት ሣራ ብእሲተ አብርሃም አውሰበ አብርሃም ካልአ ብሲ·ተ እንተ ስማ መነጠርባን ወለተ በቀጥር ንጉሠዳም።

18. ወአመከና ለይስሐቅ ፵ ዓመተ ሖረ አልአዛር ይሕስስ ሎ·ቱ ብእሲ·ተ ርብቃሃ ወሞተ አብርሃም በ፻ወ፸ ዓመ·ቱ ዓመት መቀበርዎ ውሉ·ዱ ይስሐቅ ወእስማኤል ጥቃብእሲ·ቱሣራ።

19. ወሶበኮና ለይስሐቅ አርብዓ ዓመት ፀንሰት ርብቃ ወበፅሐ ጊዜ ወሊዶታ ሆረት ሐበመልከጼዴቅ ባረካ ወጸለየ ላእሌሃ ወአስተብቁዓ በእንቲአሃ እግዚአብሔር ነበልዑል ረሰየ በከርስኪ ተባዕተ።

20. ወእሙንቱ ይከውኑ ፪ተ ይኩኑ ሊቃውንተ ላእለሕዝብ ወዘየዓቢ ይትቀነይ ለዘይንእስ ወይፃልኡ በበይናቲሆሙ ወአልቦ ማእከሌሆሙ ፍቅር እምውሉድ ዘየዓቢ ይቀትል እሁሁ።

በሚስቱ ስም ሰየማቸው።

17. ሰዎች የዚህ ንጉሥ ምስል እየሳሉ ይሠግዱ ነበር የአብርሃም ሚስት ሣራ ስለሞተች አብርሃም የዳም ንጉሥ ልጅ የሆነችው በቀጥር ልጅ መነጠርባን አግብቶ ነበር።

18. ይስሐቅ በአርባ ዓመቱ ሚስት እንዲያገባ ተፈቀደለት አልአዛርም ርብቃን ሊያገባው ሄደ አብርሃም በ፻፸ ዓመቱ መተ ልጆቹ ይስሐቅና እስማኤል ሚስቱ ሣራ ከተቀበረችበት አጠገብ ቀበሩት

19. ይስሐቅ ፵ ዓመት ሲሞላው ሚስቱ ርብቃ ፀነሰችለት የመውለጃ ጊዜዋ ሲደርስም ወደመልከጼዴቅ ሄደች መልከጼዴቅም ባረካት ስለሷም ጸለየ ወደእግዚአብሔርም ስለሷ ማለደ ልዑል እግዚአብሔር ካንቺ ሆድ ሁለት ወንዶች ልጆች ይወለዳሉ።

20. ሁለቱ ካንቺ የሚወለዱት ልጆች የሕዝብ ዓለቆች ይሆናሉ። ትልቁ ለትንሹ ይገዛል ሁለቱም በመካከላቸው ፍቅር የላቸውም እርስበርሳቸው ይጣላሉ ከትልቁ የሚወለዱት ልጆች ከትንሹ ከሚወለዱት ልጆች ጋር ይጋደላሉ።

1. ወአነ እትቀነይ ለውእቱ ብእሲ ወይሰመይ በስሙ ወልደ እግዚአብሔር ልዑል ወሕያው ወይሰቀል ከመ ደቅትል መርገመ::

22. ወሐነፀ ይስሐቅ ሀገረ ወሰመያ አይል ወአመኮኖ፳ ዓመት ሐነፅዋ ለኢያሪኮ ፯ ነገሥት፣ ንጉሠ አልገልጊን፣ ንጉሠባሳን፣ ንጉሠ አሞሬዎን ንጉሠ ገባኦን፣ ወንጉሠ ሄርገሴኖስ ንጉሠ ቀርናቤን::

23. ወሐነፅዋ ለኢያርኮ ዘዘዚአሆሙ ጥቅመ ወበውእቱ መዋዕል ንጉሠ ግብፅ ሐነፀ ሀገረ ወሰመያ ምሥሩ ወአመኮኖ ለይስሐቅ ፻ወ፴ ዓመት እንዘ፸ ዓመታቲሁ ለያዕቆብ ባረኮ እግዚአብሐር ለያዕቆብ ወተወክፈ በረከተ ይስሐቅ በሐጢአት::

24. ወእንዘ የሐውር በፍኖት ያዕቆብ ነሥአ ፯ተ አእባነ:: ወአንበሮን ወኖመ ወርእየ በሕልሙ ሰዋስወ ዘእሳት ዘይበፅሕ እስከሰማይ ወመላእክተ እግዚአብሔር የዓርጉ ወይወርዱ እንተይእቲ ሰዋስው ወእግዚአብሔር ይነብር መልእልቴሃ ወነቂሆ እምንዋሙ ይቤ ዛቲ መካን

21. ከትንሹ ልጅ ልጅ ለሚወለደው እኔ እገዛለሁ እሱም የልዑል አግዘአብሔር ልጅ ይባላል:: እሱም ሕያው ነው በዕንጨት ላይ ተሰቅሎም በአዳም ውድቀት ለሰዎች የተላለፈውን መርገም ያስወግዳል::

22. ይስሐቅ አዲስ አገርን ሠርቶ አይል ብሎ ሰየማት ይስሐቅ ስድሳ ዓመት ሲሞላው ኢያሪኮን ሰባት ነገሥታት ሠርዋት እነሱም የአልገልጊን ንጉሥ የባሳን ንጉሥ የአሞሬዎን ንጉሥ የገባኦን ንጉሥ የሄርጌሴኖን ንጉሥና የቀርናቤን ንጉሥ ናቸው::

23. እነዚህ ሰባት ነገሥታት ለየግላቸው መታሰቢያ በኢያሪኮ ላይ ሠሩ የነሱንም ባህል የተከተለው የግብፁ ንጉሥ ሌላ አገርን አቀና ያቀናውንም አገር ምሥር አለው:: ይስሐቅ መቶ ሠላሳ ዓመት ሲሞላው የያዕቆብም ዕድሜ ሰባ ዓመት በሆነ ጊዜ እግዚአብሔር ያዕቆብን ባረከው ያዕቆብ በሐጢአት የይስሐቅን በረከት ተቀበለ::

24. ያዕቆብ በጉዞ ላይ እያለ ሰባት ድንጋዮችን አሰባሰበና አስቀመጣቸው እሱም ተኛ በሕልሙም እስከሰማይ ድረስ የሚደርስ የእሳት መሰላል አየ በዚሁም የእግዚአብሔር መላእክት ይወርዱና ይወጡ ነበር:: ከእንቅፉም ሲነቃ ስለዚችው ቦታ ትንቢት ተናገረ እቺ ቦታ የልዑል እግዙአብሔር

ቤተእግዚአብሔር ይእቲ።

. ወዝንቱ ሐዋሕወ ሰማይ ወነሥኦን ለእማንቱ እእባን ወአቀሞን ምሥዋአ ለእግዚአብሔር ወቀብኦን ዘይተ ቅዱስ ወበህየ በፅአ የሀብ አሥራተ እምኩሉ ንዋዩ ቁርባነ ለእግዚአብሔር ወዛቲ ዘርእየ ያዕቆብ።

6. ኦ ወልድየ ቀሌሚንጦስ ትንቢት በእንተምፅአቱ ለክርስቶስ ወሰዋስው ዘያዕቆብ አምሳለሥቅለት ወመላእክት እንዘየዓርጉ ወይወርዱ አምሳለዘ ዜነውዎሙ ለዘካርያስ ወለማርያም ወለኖሎት ወዘነበረ እግዚአብሔር መልእልተ ሰዋስው ትእምርተልደቱ ለእግዚእነ ወመድሐኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወመካን ዘርእያ ያእቆብ አምሳለቤተክርስቲያን ይእቲ።

27. ወአእባን እለአቀሞን አርአያሃ ወአምሳሊሃ ለቅድስት ታቦት ወተቀብኦቶን በዘይት ቅዱስ አምሳሌሁ ለቅብአትስብእት ምስለ መለኮት ወዘበፅአ ያዕቆብ አሥራተንዋዩ ቁርባን ቅዱስ

28. ወሖረ ያዕቆብ እምውስተውእቱ መካን ነበላባ እሁሃ ለእሙ ወርእየ በፍኖት ዓዘቅተ አባግዕ ወክዱን አፉሃ ለዓዘቅት በዓባይ እብን።

ቦታ ትባላለችም አለ።

25. ይህ የሰማይ በር ነው ተብሏል ድንጋዮቹንም ሰበሰባቸውና ለእግዚአብሔር መሥዋእት መሠውያ አድርጎ አቀረባቸው። የተቀደሰውንም ዘይት ቀባቸው በዚሁም ከንብረቱ ሁሉ ኡሥራትን ለእግዚአብሔር ቁርባን ለመሥጠት ተሣለ ያዕቆብ ያያት ምሥጢር እቺ ናት።

26. ልጄ ቀሌሚንጦስ ሆይ ያዕቆብ ያየው ምስጢር ለወደፊት ስለነበረው ትንቢት ይገልፃል ይህም ስለክርስቶስ ወደዚህ ዓለም መምጣትን ያመለክታል መሰላሉ የክርስቶስን ስቅለት ያመለክታል የመላእክቱ መውጣት መውረድ ደግሞ የዘካርያስን የእመቤታችንንና የኖሎ ሎትንም መበሠር ያሳያል የእግዚአብሔር በመሳልል ላይ መታየት የልደቱን ምልክት ሲያሳይ ያች ያዕቆብ ያያት ቦታ ደግሞ የቤተክርስቲያን ምሳሌ በመሆን ትነገራለች።

27. ያዕቆብ ያቆማቸው ዲንጋዮች የታቦት አርአያና አምሳል ሲሆን የነሱም በቅዱስ ቅብ መቀባት የቅብዓተ ስብእት ምሳሌ ይሆናል የያዕቆብ ከገንዘቡ ከአሥር አንድ ለመሥጠት ብፅአት መግባት የቅዱስ ቁርባን ምሳሌ ነው።

28. ያእቆብ ከዚሁ ቦታ ተነስቶ ወደላባ ሄደ ላባ የናቱ ወንድም አጐቱ ነው። በመንገዱም የበጎች ዓዘቅት ጉድጓድ አየ። ይህም ዓዘቅት በከባድ ድንጋይ የተዘጋ ነበር በቀላሉ

29. ወራሄል ወለተላባ ትቀውም ህየ ምስለእሉ አባግዕ ኀበዓዘቅት ወነሥአ ያዕቆብ ወከሰታ ለይእቲ እብን እምአፈ ዓዘቅት ወነሥአ ማሕየበ ወአስተዮን ለእሉ ዕሙዓን አባግዕ እለሐለዋ ምስለራሄል ወእምዝ ቀርበ ኀቤሃ ለራኄል ወሰዓማ።

30. ወከሰተ ያዕቆብ አፈዓዘቅት አምሳለጥምቀት ቅድስት እንተ ኮነት ኀብእተ እምትካት ዘለዓለም።

31. ለቡኬ ኦ ወልድየ ቀሌሚንጦስ ከመኢክህለ ያዕቆብ ይስዓማ ለራሔል ዘእንበለዳእሙ እምድሕረከሰተ አፉሃ ለዓዘቅት ወአስተየ አባግዓ እምኔሃ ወከማሁ ይቤ አነኒ ኢርቱዕ ለሕዝብ ይባኡ ቤተክርስቲያን እንበለይጠመቁ እስመ እምድሕረተጠምቁ ይከውኑ አበግዒሁ ለክርስቶስ።

32. ሙሴኒ ነቢይ ይቤ በውስተ ኦሪት ከመያዕቆብ ተቀንየ ለላባ ፯ ዓመተ በእንተራሄል ወለቱ እንተአፍቀራ እምኵሎን አዋልዲሁ ለላባ እስመ ለራሄል ላህያ ይሴኒ እምነልያ እህታ።

33. ወከማሁ ውእቱ ሙሴ ምስለ አይሁድ እለአድሐኖሙ

ለመክፈት አይቻልም ነበር።

29. የላባ ልጅ ራሄል ከዚያ ቆማ ነበር (በጎቿን ለማጠጣት) ያዕቆብ የውኃውን ጉድጓድ የተከደነበትን ድንጋይ ከፈተና የውሃ መቅጃ ከራሄል እጅ ተቀብሎ በጎቹን ከጉድጓዱ ውሃ በመቅዳት አጠጣቸው በጎቹን አጠጥቶ ሲያበቃ ያዕቆብ ራሄልን ተመለከታት ወደሷም ቀርቦ ሳማት።

30. ያዕቆብ የውሃውን ጥልቅ ጉድጓድ መክፈቱ የቅድስት ጥምቀት ምሳሌ ነው የጥምቀት ምስጢር ረቂቅ ነውና ።

31. ልጄ ቀሌሚንጦስ ሆይ የውሃውን ጥልቅ ጉድጓድ ከፍቶ በጎቹን ከማጠጣቱ በፊት ያዕቆብ ራሄልን ሊስማት አልቻለም የጥልቅ ጉድጓዱን መክደኛ ከፍቶ በጎቹን ካጠጣ በኋላ ግን ራሄልን ሳማት እኔም የዚሁን ምሳሌ እነግርሃለሁ ሰዎች በቅድስት ጥምቀት መንፈስ ቅዱስን ሳይቀበሉ ወደቅድስት ቤተክርስቲያን መግባት ክልክል ነው። በጥምቀት የክርስቶስ በጎች ይሆናሉና።

32. ነቢዩ ሙሴም ያዕቆብ ስለራሄል ልጁ ለላባ ሰባት ዓመት እንደተገዛለት ፅፏል ያዕቆብ ከመላ የላባ ሴቶች ልጆች አብልጦ ራሄልን ስለወደዳት ነው ያዕቆብ ስለራሄል ብሎ ሰባት ዓመት ያገለገለው የራሄል መልክ ከልያ መልክ ይበልጣልና።

33. በፈርኦን እጅ ከመቀጥቀጥና ከመገዛት እግዚአብሔር በሙሴ

እግዚአብሔር እምአምልኮተ ፈርኦን፡፡

34. መቅድመ ተውህበ፡ቶ ለያዕቆብ ዘሕሱም ራእየ ልያ ወኢተውህበቶ ራሄል ዘሠናይ ራእያ ወዳግመ ኮነት ራሄል ትክድን ገፃ ከመ ኢትትረአይ ሳህያ፡፡

35. ዘሕሱም ራእያ ያኤምር እኩያን አይሁድ ዘስሕቱ በአምልኮ ጣዖት ወሐደግዎ ለእግዚአብሔር ወራሄል ትትሜሰል በዘተወክፍዎ ለእግዚአብሔር አምላክነ ወመድሐኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወአብርሃ አልባቢሆሙ ወአምለክዎ፡፡

36. ወሰበኮና ለያዕቆብ ፷ወ፱ ዓመተ ወለዶ ለሮቤል ወልዱ እምድሕሬሁ ለአህዊሁ ስሞዖን ወሌዊ ወይሁዳ ወይሳኮር ወዛብሎን ወዮሴፍ ወብንያም ወጋድ ወአሴር ወዳን ወንፍታሌም ውሉድ ዘፀገዎ እግዚአብሔር ለያዕቆብ፡፡

37. ወአመኮና ለያዕቆብ ፻ወ፳ ዓመተ ሞተ ይስሐቅ አቡሁ ወገነዝዎ ደቂቁ ያዕቆብ ወኤሳው ወቀበርዎ ጥቃመቃብረአቡሁ ለአብርሃም፡፡

38. ወእምዝ ሞተት ልያ ብእሲቱ ለያዕቆብ ወቀበርዋ ጥቃ መቃብሪሁ ለአብርሃም ወእምዝ አውሰባ ይሁዳ ለብእሲት ከነዓናዊት ወበእንተዝ ሐዘነ ዓቢየ ሐዘነ ያእቆብ ወይቤሎ

መሪነት አይሁድን ያዳነበትንም ምሥጢር በዚሁ ይገልፃል፡፡

34. ላባ ለያዕቆብ እንዲያገባት በቅድሚያ የፈቀደለት መልከመልካሟን ራሄል ሳይሆን መልከጥፉዋን ልያ ነው ያገባው በሌላ በኩል መልከቀናዋ ልያ ራሷን ትከናነብ ነበር (ውበቷን ላለማሳየት)፡፡

35. መጥፎ መልክ ያላት ልያ የአይሁድ በአምልኮ ጣኦት መጠመድንና ከእግዚአብሔር መንገድ መውጣትን ያመለክታል፡፡ ራሄልም ጌታችንንና መድሐኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስን ባመኑና ልቡናቸውንም እግዚአብሔር ያበራላቸውን ምእመናን ትመሰላለች፡፡

36. ያዕቆብ የስድሳዘጠኝ ዓመት ዕድሜ ሰው ሲሆን ሮቤልን ወለደው ከሱ በማከታተል የሮቤልን ወንድሞች ስምዖንን ሌዊን ይሁዳን ይሳኮርን ዛብሎንን ዮሴፍን ብንያምን ጋድን አሴርን ዳንን ንፍታሌምን ወለዳቸው እነዚህ አሥራ ሁለት ልጆች እግዚአብሔር ለያዕቆብ የሠጣቸው በረከቶች ናቸው፡፡

37. የይስሐቅ ዕድሜ መቶሃያ ዓመት ሲሆን ይስሐቅ ሞተ፡፡ ልጆቹ ኤሳውና ያዕቆብም አባታቸውን ይስሐቅን ገነዙት አባቱ አብርሃም ከተቀበረበት መቃብር አጠገብም ቀበሩት፡፡

38. የያዕቆብሚስት ልያ ሞተችና ከአብርሃም መቃብር አጠገብ ቀበሩዋት የያዕቆብ ልጅ ይሁዳ ከነዓናዊት የሆነችውን ሴት በሚስትነት አገባ በዚሁም ያዕቆብ ከባድ ሐዘንን አዘነ ለልጁ

ለይሁዳ ወልዱ በአምላክአብርሃም ይስሐቅ ከመኢትደመር ምስሌነ ዘርአከነዓናውያን

39. ይሁዳሰ አበዮ ወኢሰምዓ ቃሎ ዉውእቱ ኢወለደ እምኔሃ እስመ እግዚአብሔር ልዑል ሰምዓ አስተበቁአቶ ለያዕቆብ ወኢደመረ ዘርአከነዓናውያን ምስለዘርኡ።

40. ወእምዝ ሰከበ ይሁዳ ምስለ ትእማር ወወለደቶሙ ለፋሬስ ወለዛራ በእማንቱ መዋዕል ሆረ ያዕቆብ ምስለ ደቂቁ ውስተ ምድረ ግብፅ ወነበሩ ፲ወ፪ ዓመተ ወሰበ ኮኖ ለያዕቆብ ፻ወ፵ ዓመተ ሞተ እንዘዓመታቲሁ ለዮሴፍ ፶ወ፪ ዓመት ገነዞ ዮሴፍ ወልዱ ወቀበሮ በምድረ ግብፅ።

41. ወእምድሕረ ፶ወ፪ ዓመት አግአዘ ዮሴፍ ሥጋሁ ለያዕቆብ አቡሁ ወአብፅሖ ኀበመቃብረ አበዊሁ አብርሃም ወይስሐቅ።

42. ይሁዳ ወለዶ ለፋሬስ ወፋሬስ ወለዶ ለኤስሮም ወኤሥሮም ወለዶ ለአራም ወአራም ወለዶ ለአሚናዳብ ወአሚናዳብ ወለዶ ለነአሶን።

43. ነአሶን የዓቢ እምኵሉ ትውልደ ይሁዳ ወአሚናደብ አውሰበ ወለቶ ለአልአዛር ወልደ አሮን ካህን ወእምነ

ይሁዳም ባባቶቹ አብርሃምና ይስሐቅ ስም እቺን ሴት ከዘሮቹ እንዳትጨመር አለው።

39. ይሁዳ ግን የያዕቆብን ምክር አልሰማም ሆኖም ከከነዓናዊቷ ልጅ አልወለደም ልዑል እግዚአብሔር የያዕቆብን ልመና ሰምቷልና የከነናውያንም ዘር ከነገደ አብርሃም እንዲጨመሩ አላደረገም።

40. ይሁዳ ትእማርን ተገናኛት ከሷም ፋሬስንና ዛራን ወለደ በዚሁ ወቅት ያዕቆብ ከልጆቹ ጋር ወደምድረ ግብፅ ሄደ አሥራ ሁለት ዓመትም በግብፅ ኖሩ ያዕቆብ አንድ መቶ አርባ ዓመት ሲሞላው ሞተ በዚህ ጊዜ የዮሴፍ ዕድሜ አምሳሁለት ዓመት ሁኖ ነበር ስለዚህ አባቱ ያዕቆብን ገነዘው ለጊዜውም ባለበት ምድረ ግብፅ ቀበረው።

41. ካምሳ ሁለት ዓመት በኋላ ዮሴፍ ያባቱ ያዕቆብን ዓፅም ከግብፅ አፍልሶ ወደከነዓን በመውሰድ ባባቶቹ አብርሃምና ይስሐቅ መቃብር ላይ ቀበረው።

42. ይሁዳ ፋሬስን ወለደ ፋሬስ ኤስሮምን ወለደው ኤሥሮም አራሞን ወለደው አራም አሚናዳብን ወለደው አሚናዳብ ነአሶንን ወለደው።

43. ከይሁዳ ትውድ ሁሉ የነአሶን ይበልጣል የነአሶን አባት አሚናዳብ የካህኑ አሮን አልአዛር ልጅን አግብቷል። ከሷም

አሚናደብ ኮነ ክህነት ውስተቤተ እሥራኤል ወእምነነ አሶን ኮነ ውስቴቶሙ መንግሥት።

44. ለቡ ኦ ወልድየ ቀሌሚንጦስ ዘከመኮነ መንግሥት እምይሁዳ ነአሶን ወለደ ለሰልሞን ወሰልሞን ወለዶ ለቦኤዝ እምራኬብ ወእሞትዝምደ ነገሥት ይእቲ።

45. እግዚአብሔር ልዑል ኢያርኰሶ ለሎጥ በእንተዘሰከበ ምስለአዋልዲሁ ወኢኮነ ሳእሌሁ ነውረ። አላ ውእቱ ሠናየ ገብረ በእንተዘረድኦ ለአብርሃም በውስተነግድ ወተወክፎሙ ለመላእክት በአሚን።

46. ወበእንተዝ ረሰየ እግዚአብሔር ነገሥተ እምራኬብ ዘእምዘርአሎጥ ወእምውሉ ደዚአሁ ኮነት ብእሲቱ ለሰሎሞን ወልደ ዳዊት ዘእምዘርአ አብርሃም እስመአው ሰበ ሰሎሞን ፺፻ አንስተ ዕቁባተ።

47. ወኢረከበ በውስቴቶን ውሉደ ወኢአሐደ እምኔሆን እስመ እግዚአብሔር ልዑል ኢሠምረ ይደመር ዘርኦሙ ለከነናውያን ምስለዘርአሕሩይ ሕዝብ ዘእምኔሆሙ ተሰብአ እግዚኤነ ኢየሱስ ክርስቶስ።

ፊኒሐስ ካህንን ወለደው ስለዚህ የቤተ እሥራኤል ክህነት ከአሚናዳብ ተመሠረተ። ከነአሶን ደግሞ የቤተእስራኤል መንግሥት ተመሠረተ።

44. ልጄ ቀሌሚንጦስ ሆይ መንግሥት በይሁዳ ለእሥራኤል ልጆች እንደተመሠረተ አስተውል ነአሶን ሰልሞንን ወለደው ሰልሞን ከራኬብ ቦኤዝን ወለደው ራኬብ የነገሥታት ዘር ናት።

45. ልዑል እግዙአብሔር ሎጥን ከሴቶች ልጆቹ ጋር የግብረሥጋ ግንኙነት በማድረጉ አላረከሰውም ነውር ሁኖም አልተቈጠረበትም አብርሃምን ተከትሎ ካገሩ በመውጣቱና ከሰዶም በመላእክት ትእዛዝ ሳያቅማማ በመውጣቱ በእግዚአብሔር ዘንድ ታላቅ ነው።

46. ስለዚህ ራኬብ ከሎጥ ከተነሱ ነገሥታት ትውልድ ያላት ናት። ከነዚሁም ሲያያዝ መጥቶ ከራኬብ ዘር የሆነችውን ሚስት የዳዊት ልጅ ሰሎሞን አግብቷል። ሰሎሞን ከአብርሃም ዘር መሆኑ ሲታወቅ ሰባት መቶ ዕቁባቶችን አግብቶ በንጉሥነት ተቀምጦ ነበር።

47. ሰሎሞን ግን ከነዚህ ሁሉ ዕቁባቶቹ አንድ ልጅ እንኳ አልወለደም ልዑል እግዙአብሔር የከነናውያን ዘር ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ሥጋን ከሚለብስባቸው የተመረጡ ሕዝቦች ጋር አንድ ለማድረግና ለማቀላቀል (ለማደባለቅ) አልፈለገምና።

48. ኵሎንኬ አንስቲያሁ ለሰሎሞን እምዘርአከነአን እማንቱ ዜናሁሰ ለሙሴ ነቢየ እግዚአብሔር መጻሕፍት ቅዱሳት ይዜንው ከመሌዊ ሶበሆረ ምስለአቡሁ ብሔረግብፅ ሙሴ ወትእማር ወኢያሱ ወልደነዌ ወካሌብ እምዘርአዚአሁ።

49. ወለሙሴ ሶበወረውዎ ውስተ ተከዚ ነስአቶ ሰፌር ወለተፈርኦን ወእተወቶ ቤታ ወሰበኮና ፵ ዓመተ ቀተሎ ለናቦም ግብፃዊ ሊቀቀዳሕያኒሁ ለፈርኦን ወጐየ ኀበራጉኤል ካህነ ምድያም።

50. ወበህየ አውሰበ እኅቶ ለራጉኤል ወወለደ ፪ ውሉደ ወሰበኮና ለሙሴ ፶ወ፪ ዓመተ ወኩሉ መዋዕለ ሕይወቱ ፻ወ፳ ዓመት ወነበረ በምድረ ግብፅ ፵ ዓመተ ወበምድረምድያም ፵ ዓመተ ወኮነኖሙ ለደቂቀ እሥራኤል ፵ ዓመተ በውስተገዳም።

51. ወእምድሕረሞተ ሙሴ ኰነኖሙ ለሕዝብ ኤያሱ ወልደነዌ ፴ወ፬ ዓመተ ወእምድሕሬሁ ኰነኖሙ ኩስ ዕልው ፰ ዓመተ ወእምድሕሬሁ ጎትያንያል ወልደቄኔዝ እሁሁ ለካሌብ ፳ ዓመተ ወእምድሕሬሁ ተቀንዩ ደቂቀ ፳ል ለኤግሎሞ ንጉሠ ሞአብ ፲ወ፰ ዓመተ።

52. ወእሞዝ አድሐኖሙ እግዚአብሔር እሞእዴሁ

48. የሰሎሞን ሚስቶች በሙሉ ከምድረከነአን ዘሮች ነበሩ የሙሴ ታሪክ ቅዱሳት መጻሕፍት እንደሚነግሩን የያዕቆብ ልጅ ሌዊ ካባቱ ያዕቆብ ጋር ወደግብፅ ሄደ ከዝያው ስለቀረ ከሱ ዘሮች ሙሴ ትእማርንና የነዌ ልጅ ኢያሱና ካሌብ በምድረ ግብፅ የእሥራኤል ልጆች እያሉ ተወለዱ።

49. ሙሴ ወደወንዝ ውሃ በተጣለ ጊዜ ሰፌር የተባለችው የፈርኦን ሴት ልጅ ወስዳ ከቤቷ አሳደገችው ሙሴ አርባ ዓመት ሲሞላው "ናቦም" የተባለውን የፈርኦን የመጠጥ አለቃ ገደለውና ራጉኤል ወደተባለው የምድያም ካህን ሸሸ።

50. በዚሁ የራጉኤልን እህት አግብቶ ሁለት ልጆችን ወለደ ሁለቱን ልጆች የወለዳቸው በአምሳሁለት ዓመቱ ነው የሙሴ ጠቅላላ ዕድሜ መቶ ሃያ ዓመት ሲሆን በምድረግብፅ አርባ ዓመት በምድረምድያም ፵ዓመት እስራኤልን በምድረበዳ እየመራ ፵ ዓመት ኑሯል።

51. ሙሴ ከሞተ በኋላ የነዌ ልጅ ኤያሱ ሰላሳ አራት ዓመት እስራኤሎችን ገዛቸው ከሱ ቀጥሎ ከሐዲው ኩስ ስድሳ ዓመት ገዛቸው ከሱ ቀጥሎ ጎቶልያንያል ወልደ ቄፋዝ የካሌብ ልጅ ሃያ ዓመት ገዛቸው ከዚያ በኋላ ላንድ መቶ ስድሳ ዓመት በኤግሎሞ ንጉሠሞአብና በተከታዮቹ መቶ ስድሳ ዓመት እስራኤላውያን ሲገዙ ኖሩ።

52. ከሱም እጅ እግዚአብሐር አዳናቸው ከሱ በኋላ የጌራ ልጅ ናኦድ

ወእሞድሕሬሁ ኰነኖሙ ናኦድ ወልደጌራ ፹ ዓመተ ወበ፳ወ፯ ዓመተሞኩናኑ ለናኦድ ተፈፀመ ፵፻ እምፍጥረት ወእምድኅሬሁ፡፡ ኰነኖሙ ኢያሜን ፳ወ፫ ዓመተ፡፡

53. ወእምድሕሬሁ ኰነንዎሙ ዲቦራ ወባርቅ ፵ ዓመተ ወእምድሕሬሆሙ ኰነንዎሙ ሰብአምድያም ፯ ዓመተ ወአድሐኖሙ በእዴሁ ለጌዴዎን ፵ ዓመተ ወእምድሕሬሁ ኰነኖሙ አቤሜሌክ ፫ ዓመተ ወእምድሕሬሁ ኰነኖሙ ቱላ ወልደፉሕ ፳ወ፫ ዓመተ፡፡

54. ወቆመ እምድሕሬሁ ኢያኤር ገለአዳዊ ወኰነኖሙ ለ፳ኤል ፳ወ፪ ዓመተ ወእምድሕሬሁ ቀነዩዎሙ ኤሎፍሊ ፲ወ፰ ዓመተ ወእምድሕሬሁ አድሐኖሙ በእዴሁ ለዮፍታሄ ዘሦአ ወለቶ፡፡

55. ወኰነኖሙ ዮፍታሄ ፯ ዓመተ ወእምድሕሬሁ ሐሴቦን ኰነኖሙ ፯ ዓመተ ወእምድሕሬሁ ኰነኖሙ ኤሎም ፵ ዓመተ ወእምድሕሬሁ ቀነዩዎሙ ኢሎፍሊ ፵ ዓመተ፡፡ ወእምድሕሬሁ ኰነኖሙ ኤሎም ዘቡላዊ ፵ዓመተ ወእምድሕሬሁ ቀነዩዎሙ ኢሎፍሊ ፵ዓመተ፡፡

56. ወእምድሕሬሁ አድሐኖሙ እግዚአብሔር በእዴሁ

ሰማንያ ዓመት ሙሉ ገዛቸው ከዚሁ መካከል በሃያ ሰባተኛው ዓመተ መንግሥቱ ፍጥረት ከተጀመረ አራትሺ ዓመት ሞላ፡፡ ከናኦድ በኋላ ሕዝበእስራኤልን የገዛው ኢያሜን ይባላል፡፡ ኢያሜን ሃያ አምስት ዓመት ገዝቷቸዋል፡፡

53. ከዚያ ዲቦራና ባርቅ አርባ ዓመት ገዙዋቸው፡፡ ከነሱ በኋላ ምድያማውያን ሰባት ዓመት ገዙዋቸው ከነሱም እጅ እግዚአብሔር አዳናቸው፡፡ ያዳናቸውም በጌዴዎን አማካይነት ነው፡፡ ጌዴዎን በበኩሉ እስራኤላውያንን አርባ ዓመት ገዝቶአቸዋል ከሱ በኋላ አቤሜሌክ መቶ ዓመት ገዝቶአቸዋል ከሱ ቀጥሎ ቱላ ወልደፉሕ ሃያ አምስት ዓመት ገዝቶአቸዋል፡፡

54. ከሱ ቀጥሎ ኢያኤር ገለአዳዊ ሃያሁለት ዓመት ገዛቸው ከሱ ቀጥሎ ኤሎፍላውያን አሥራ ስምንት ዓመት ገዙቸዋቸው ከነሱም እጅ እግዚአብሔር ልጁን በሰዋው ዮፍታሄ አማካይነት አዳናቸው፡፡

55. ዮፍታሄ እስራኤላውያንን ሰባት ዓመት ገዛቸው ከሱ ቀጥሎ ሄሴቦን ሰባት ዓመት ገዛቸው ከሄሴቦን ቀጥሎ ኤሎም አርባ ዓመት ገዛቸው ከሱ ቀጥለው ኢሎፍላውያን አርባ ዓመት ገዙዋቸው ከኢሎፍላውያን ቀጥሎ ኤሎም ዘቡላዊ ፵ ዓመት ገዛቸው ከኤሎም ዘቡላዊ ቀጥለው ኢሎፍላውያን አርባ ዓመት ገዙዋቸው፡፡

56. ከሱ ቀጥሎ እግዚአብሔር በኃይለኛው ሶምሶን እጅ

ለሶምሶን ኃያል ወኮነኖሙ ሶምሶን ፲ወ፪ ዓመተ ለሕዝብ ወእምዝ ሀነሁ ደቂቀ እስራኤል ፲ወ፪ ዓመተ እንዘአልቦሙ መኮንን። ወእምድሕረዝ ተንሥአ ኤሊ ካህን ወኮነኖሙ ፵ ዓመተ ወእምድሕሬሁ ኮነኖሙ ሣሙኤል ነቢይ ፪ ዓመተ።

57. ወእምዝ ገብሩ ሕዝብ እኩየ ቅድመ እግዚአብሔር ወአንገሡ ላዕሌሆሙ ሣኦልሃ ውእቱ ዘነግሠ ቀዳሚ ላዕለ ደቂቀ እሥራኤል ወኮነኖሙ ፵ ዓመተ በመዋዕሊሁ አስተርአየ ጎልያድ ሐያል ወኢማሰኖሙ ለደቂቀ ፳ ኤል ወቀተለ ወራዙቶሙ።

58. ወእምዝ ፈነዎ እግዚአብሔር ዳዊት ነቢየ ወቀተሎ። ወቀተልዎ ለሣኦል ኢሎፍሊ እስመሐደጎ ለእግዚአብሔር ወአስተብቁዓ ነበአጋንንት ወእምድሕሬሁ ነግሠ ዳዊት ወልደ እሴይ ፵ ዓመተ ላዕለእሥራኤል ወእምድሕሬሁ ነግሠ ሰሎሞን ወልዱ ወገብረ ዓበይተ ግብራተ ወፈነወ ውስተ ሀገረ አውቂር ብዙሐነ አሕማረ ዘይፀውሩ እምይእቲ ሀገር ፵ወ፯ አውራሐ።

59. ወሐነፀ ብዙሐነ አህጉረ ወአዲ ሐነፀ ዓቢየ ሀገረ በውስተገዳም ወሰመያ ሀገረፀሐይ ወፈድፈደ ክብሩ ለሰሎሞን ወተሰምዓ ዜናሁ ውስተኩሉ በሐውርት ወበዝሐ ጥበቡ ወክቡሩ ወብዕሉ።

ከኢሎፍላውያን እጅ አዳናቸው ስለዚህ ሶምሶን አሥራ ሁለት ዓመት ገዛቸው። ከሶምሶን በኋላ ግን ደቂቀ እሥራኤል ገገር ሳይኖራቸው አሥራ ሁለት ዓመት ኖሩ ከአሥራ ሁለት ዓመት ያለገዢ መኖር በኋላ ካህኑ ኤሊ ተነስቶ አርባ ዓመት ገዛቸው ከኤሊ ቀጥሎ ነቢዩ ሳሙኤል አሥራ ሁለት ዓመት ገዛቸው።

57. በዚህ ጊዜ ሕዝበ እስራኤል ክፉ ሥራን ሠሩ እግዚአብሔርንም አስቀየሙ በላያቸውም ላይ ሣኦልን አነገሱ ሳኦል የእስራኤል የመጀመርያው ንጉሥ ነው አርባ ዓመትንም ገዟቸዋል በዘመኑ ጎልያድ የሚባል ኃይለኛ ተነስቶ እስራኤላውያን አስጨንቆአቸዋል ብዙዎች ወጣቶቻቸውንም ገድሎባቸዋል።

58. ከዚያ በኋላ እግዚአብሔር ዳዊትን ላከ ዳዊትም ጎልያድን ገደለው ሳኦልን ደግሞ እግዚአብሐርን ትቶ በአጋንንት ስላሟረተ ኢሎፍላውያን ገደሉት ከሳኦል ቀጥሎ ነቢዩ የእሴይ ልጅ ዳዊት ፵ ዓመት ነገሠ ከዳዊት ቀጥሎ ሰሎሞን ነገሠ ሰሎሞን ብዙ ታላላቅ ሥራዎችን ሠርቷል ሰሎሞን ለአርባ ሰባት ዓመት ሙሉ አውቂር ወደተባለው አገር መርከቦችን እየላከ ወርቅን አስጫነ።

59. ሰሎሞን ብዙ አገሮችን አቅንቷል በምድረበዳው ውስጥ ትልቅ አገርን ሠራና ሀገረ ፀሐይ ብሎ ሰየማት የሰሎሞን ክብር እጅግ በዛ ዝናውም በብሔሮች ሁሉ ተሰማ ጥበቡና ክብሩ እጅግ የላቀ ሁኖ ታየ።

60. ወመፅአት ኀቤሁ ንግሥተ አዜብ ወተአዘዘት ሎቱ። ወአዲ መፅአ ኀቤሁ ኀብራን ንጉሠ ጢሮስ ወሲዶና ወአፍቀሮ ፈድፋደ ወረድኦ ወገብረ ፈቃዶ ለሰሎሞን እስመ ውእቱ ያፈቅሮ ፈድፋደ ለዳዊት አቡሁ። ወመንግሥቱሰ ለዳዊት እምቅድመ መንግሥቱ።

61. ወአውሰበ ሰሎሞን ፲፻ አንስተ ወሶበ አፍቀሮን ፈድፋደ አማሰነ ጥበቢሁ ወሜጣሁ እምአምልኮ እግዚአብሔር ውስተ አምልኮ ጣዖት። ወሞተ እምድሕረነግሠ ፵ ዓመተ።

62. ወአዲ ኀብራን ንጉሠ ጢሮስ ወሲዶና ስሕተ ወክህዶ ለእግዚአብሔር ወሰመየ ርእሶ እግዚአብሔር ወይቤ አነሰ እነብር ውስተልበ አብሕርት ከመአምላክ ወሶበሰምዓ ዜናሁ ናቡከደነፆር ንጉሥ ወሐረ ኀቤሁ ወቀተሎ።

63. ወረኩሰት ምድር በአምልኮ ጣዖት ወበዝሙት። ውስተ ኢየሩሳሌም መሥዋዕተ አጋንንት ተሠአ። ወበመዋዕሊሁ ተናፈቀ መንግሥተ ቤተዳዊት ወኮነ ፪ ክፍለ። ወበሐምስ ዓመተ መንግሥቱ ሆረሴሳን ንጉሠ ግብፅ መፅአ ውስተ ኢየሩሳሌም ወማሕረከ ኵሎ ዘሀሎ ውስተ ቤተ እግዚአብሔር።

60. የአዜብ ንግሥት ወደሰሎሞን መጣች ለሱም ታዘዘች እንደገና ኀብራን የተባለው የጢሮስና የሲዶና ንጉሥ ወደሰሎሞን መጣ እጅግም ሰሎሞንን ወደደው ረዳውም ፈቃዱንም ሁሉ አደረገ ይህ ኀብራን የተባለው ንጉሥ የሰሎሞንን አባት ዳዊትን እጅግ ይወደው ነበር ነገር ግን ከኀብራን አስቀድሞ ነው ዳዊት የነገሠው።

61. ሰሎሞን አንድ ሺ ሚቶችን አገባ እጅግም ስለወደዳቸው ጥበቡን አጠፋ። እነዚህም ሴቶች እግዙአብሔርን ከማምለክ አውጥተው ጣዖትን እንዲያመልክ አደረጉ ሰሎሞን በንጉሥነት አርባ ዓመት ሲገዛ ቈይቶ ሞተ።

62. ኀብራን የተባለው የጢሮስና የሲዶና ንጉሥ የሰሎሞንን በአምልኮ ጣዖት መበከል ሲያይ እግዚአብሔርን ካደው እኔ እግዚአብሔር ነኝም አለ በባሕሮች ውስጥም የመኖር ችሎታ አለኝ አምላክ ነኝና አለ። ናቡከደነፆር ንጉሥ የኀብራን እግዚአብሔርን መካድ ሲሰማ ሄዶ ገደለው።

63. ሰሎሞን ሲሞት ልጁ ሮብአም ነገሠ በዚሁ ወቅት ምድር በአምልኮ ጣዖትና በዝሙት ረከሰች በኢየሩሳሌም ሰዎች ለአጋንንት መሥዋዕትን ሠው። በሮብአም ዘመን የዳዊት መንግሥት ለሁለት ተከፈለች። ሁለት መንግሥታትም ሆኑ ባምስተኛው የሮብአም ዘመነመንግሥት ሴሳን የተባለው የግብፅ ንጉሥ ኢየሩሳሌምን ወረረና በቤተ እግዚአብሔር የነበረውን

64. ወነሥአ ኵሎ ንዋየ ወርቅ ወብሩር ዘዘገቡ ዳዊት ወሰሎሞን ወፀንዑ ፈድፋደ ወይቤሎሙ ለአይሁድ ኢኮነ ንዋየ ወርቅ ወብሩር ዘአጥረዩ ለሊሆሙ አሉ እሙንቱ ዘአምፅኡ አበዊክሙ እምድረግብፅ አመጉዩ እምገፀፈርኦን፡፡

65. ወሞተ ሮብአም ወልደሰሎሞን ወኮነ መዋዕለ መንግሥቱ ፲ወ፯ ዓመተ፡፡ ወእምድሕሬሁ ነግሠ አቢይ ወልዱ እንዘ ፫ ዓመታቲሁ ወገብረ እኩየ ቅድመ እግዚአብሔር ወሞተ፡፡

66. ወእምድሕረ ፵ ዓመት ነግሠ ድሕሬሁ አሳ ወልዱ ወገብረሠናየ ቅድመ እግዚአብሔር ወአፅርዓ አምልኮ ጣዖት ወአእተተ ዝሙተ እምኢየሩሳሌም ወሰደዳ ለእሙ እመንግሥቱ እስመሐነፀት ቤተ አማልክት ወኮነ መዋዕለ መንግሥቱ ፫ ዓመት ወእምድሕሬሁ ነግሠ ወልዱ ዮሳፍጥ፡፡

67. ወኢሆረ ዮሳፍጥ በፍኖተ አቡሁ ወአፍቀሮሙ ለሰብአቤተ አክአብ ወገብረ ርስተ ምስሌሆሙ ወሐነፀ ብዙሐነ አሕማረ ወፈነዎሙ ውስተ ሀገረ አውቂር ከመይፁሩ ወርቀ ወያምፅኡ ሎቱ እምዛቲ ሀገር፡፡ ወአስጠሞን እግዚአብሔር ለአሕማሪሁ ውስተባሕር፡፡

ንብረት ሁሉ ዘረፈ፡፡

64. ዳዊትና ሰሎሞን በከባድ ጥረትና ድካም በቤተመቅደስ ያከማቹትን ወርቅና ብር አንድም ሳያስቀር ወሰደው ለአይሁድም "ይህ ወርቅና ብር የዳዊትና የሰሎሞን ንብረት አይደለም አባቶቻችሁ ከፈርኦን ግዛት ሸሽተው በወጡ ጊዜ ከግብፅ ይዘውት የመጡ የግብፃውያን ሐብት ነው" አላቸው፡፡

65. የሰሎሞን ልጅ ሮብአም ሞተ የግዛት ዘመኑም አሥራሰባት ዓመት ነው ከሱ ቀጥሎ አብያ የተባለው ልጁ ነገሠ አብያ ሲነግሥ የሃያ ዓመት ልጅ ነበር በእግዚአብሔር ፊትም ክፉ ሥራ ሠራ ሞተም፡፡

66. እሥራኤሎች አርባ ዓመት ያለንጉሥ ከቆዩ በኋላ የአብያ ልጅ አሳ ነገሠ በእግዚአብሔር ፊትም መልካም ሥራን ሠራ አምልኮ ጣዖትን አስወገደ ዝሙትንም አጠፋ የገዛ እናቱንም የጣዖት ማምለኪያ ሥለሠራች ከኢየሩሳሌም አባረራት የመንግሥቱ ዘመን ሃያ ዓመት ነው እሱ ከሞተ በኋላ ልጁ ዮሳፍጥ የሱን መንግሥት ወረሰ፡፡

67. ዮሳፍጥ ባባቱ መንገድ አልሄደም የአክ አብን ቤተሰቦች ወደዳቸው ከነሱ ጋርም ርስት መካፈል ጀመረ ብዙ መርከቦችንም ሠራና እንደሰሎሞን ወርቅን ተጭነው ይመጡ ዘንድ አውቂር ወደተባለው አገር ላካቸው እግዚአብሔር ግን መርከቦቹን ወደባሕር አሰጠማቸው፡፡

68.. ወኮነ መዋዕለ መንግሥቱ ፳ ዓመት ወእምድሕሬሁ ነግሠ ወልዱ ኢዮራም እንዘዓመታኒሁ ፴ ክረምት።

## ምዕራፍ ፮ ጴጥሮስ ከሠተ ለቀሌሚንጦስ ረድኡ ብዙሐተ ምሥጢራተ እግዚአብሔር

1. በስመአብ ወወልድ ወመንፈ ስቅዱስ ፩ አምላክ ዘከሠተ ጴጥሮስ ለረድኡ ቀሌሚንጦስ ይቤ ቅዱስ ጴጥሮስ ለረድኡ ቀሌሚንጦስ ሶበተፈፀመ ፵ ዕለት እምድሕረትንሣኤሁ ለእግዚእነ ወመድሐኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ ፈቀደ ይዕርግ ውስተ ሰማያት ወይትመየጥ ውስቲስብሐቲሁ ወግሩም ማሕደሩ። ወእምዝ አዕረገነ ውስተደብር ቅዱስ።

2. ወእምዝ ነሥአኒ ሊተ ወለያዕቆብ ወለዮሐንስ ደቂቀ ዘብዴዎስ ወለማርያም ቅድስት ወአዕረገነ ምስሌሁ ወሐደጎሙ ለእለተረፉ አርድእት ታሕተደብር ወነፍሐ ላእሌነ ወይቤለነ ንሥኡ ኃብተ መንፈስቅዱስ ወአዲ ይቤለነ ኢታጥርዩ ወርቀ ወኢብሩረ ወኢስንቀ ለፍኖት እንዘተሐውሩ ውስቴታ። ወኢትፁሩ በትረ ወኢትፍቅዱ

69. ዮሳፍጥ ሃያ ዓመት በንጉሥነት ቈይቶ ሞተ ከሱ በኋላ ልጁ ኢዮራም በሰላሳ ዓመት ዕድሜው ነገሠ።

## ምዕራፍ ፮ ጴጥሮስ ለተማሪው ቀሌሚንጦስ ብዙ ምሥጢራተ እግዚአብሔርን ገለፀለት

1. በአብ በወልድ በመንፈስ ቅዱስ ስም አንድ አምላክ። ይህ ጴጥሮስ ለተማሪው ቀሌሚንጦስ ብዙ ምሥጢርን የገለፀበት ዝግጅት ነው። "ጌታችን መድሐኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከትንሣኤው በኋላ በአርባኛው ቀን ወደሰማያት ያርግ ዘንድና ተመልሶ ግሩምና አስደናቂ እንዲሁም የመላእክትና የሊቃነመላእክት የማያቋርጥ ምሥጋና ወደሚሰማበት ሰማያዊ መንበሩ በምሥጋናና በታላቅ አምላካዊ ክብር ያርግ ዘንድ በወደደ ጊዜ በዛንጊዜ ወደተቀደሰው ተራራ አወጣን" እያለ ቅዱስ ጴጥሮስ ንግግሩን ቀጠለ።

2. እንዲህም አለ "እኔን የዘብዴዎስን ልጆች ያዕቆብንና ዮሐንስንና ቅድስት ድንግል ማርያምን ወሰደን የቀሩትን ሐዋርያት ደግሞ ተዋቸው ከተራራው እግርጌም እንዲቈዩ አዘዛቸው። እኛን ግን እፍ አለብን መንፈስ ቅዱስንም አሳደረብን ከዚህም አያይዞ እንዲህ አለን "ወርቅንና ብርን አታከማቹ ስንቅንም አትሸከሙ በምትጓዙበት አገር ሁሉ በእጃችሁ በትርም ይሁን ሌላ

ዘንተ ኩሎ።

3. ወአእምሩ ከመወሀብኩክሙ ሥልጣነ ታንብሩ እደዊክሙ ዲበዱያን ዱያነ ፈወሱ። ወሙታነ አንሥኡ እስመንብተመንፈስቅዱስ ይከውነክሙ ሥልጣነ ውስተኩሉ ምድር ወናሁ እፌንወክሙ ኀበአዘዘኒ አብ ወሀብኩክሙ ሠናያተ ኃብተ በፀጋ ወአንትሙኒ በፀጋ ሀቡ። ወበንበተጋባእክሙ በስመዚአየ አነ እሄሉ ምስሌክሙ።

4. ወእምዝ ይቤለኒ ቅዱስ መምህርየ ኦ ቀሌሚንጦስ ዝንቱ ምሥጢር ዘተሐስበ እምኔየ ዓቢይ ውእቱ ወኢይትከሰት ለኩሉ ሰብእ እስመእግዚእነ ኢየሱስ ክራስቶስ አለበወነ ዘንተ ምሥጢረ እምቅድመ ዕርገቱ ኢርቱዕ እክስት ለከ እስመኢትክል ፀዊሮቶ።

5. ወእምዝ አሐዝኩ አነ ቀሌሚንጦስ እሥአል ኀበመምህርየ ቅዱስ ጴጥሮስ ከመያለብወኒ ኩሎ ዘከሰተ ሎቱ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወሶበርእየ ጴጥሮስ ከመእሥእል ኀቤሁ በዓፅር ወበአንብዕ ወይቤለኒ አምፅእ ክርታስ ወፀሐፍ ኩሎ ዘእከሥት ለከ።

6. ወእምዝ ነሥአኒ ወዓዕረገኒ ውስተደብረዘይት ውስተ መካነ ዘዓርገ እግዙእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ውስተሰማይ በከየ

ፊዕማችሁ አትያዙ"

3. በበሽተኞች ላይ እጃችሁን በማሳረፍ ትፈውሱዋቸው ዘንድ ሙታንን ታነሱ ዘንድ የመንፈስቅዱስ ኃብት ከኔ ዘንድ ተሠጥቶአቹኋል። ይህንንም ሀብት ከምድር በመላ በምትሄዱበት ሁሉ እንጂ በተወሰነ ቦታ ብቻ አይደለም። አሁንም ፀጋን ሠጥቻችሁ አለሁ እናንተም በፀጋ የተቀበላችሁትን ሁሉ በፀጋ ሥጡ በስሜ በተሰበሰባችሁበት ሁሉ እኔም ከናንተ ማህል እገኛለሁ።

4. ቀሌሚንጦስ እንዲህ አለ "መምህሬ ጴጥሮስ ቀሌሚንጦስ ሆይ እኔ እንድገልፅልህ የምትፈልገው ሁሉ እጅግ ከባድ ነው ለሰው ሁሉም የሚገለፅ አይደለም ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ወደሰማያት ከማረጉ አስቀድሞ ይህን ምሥጢር ገልፆልናልና ስለዚሁ ሁሉን ዘርዝሬ እገልፅልህ ዘንድ አይገባም ልትሸከመው አትችልምና"

5. ከዚህም በመቀጠል እኔ ቀሌሚንጦስ ወደመምህሬ ጴጥሮስ ልመናየን ቀጠልኩ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ የገለፀለትን ሁሉ ያስረዳኝ ዘንድ መምህሬ ጴጥሮስም ከሱ ዘንድ ብዙ ምሥጢርን ለማወቅ እንደጓጓሁ ተረድቶ እያለቀስኩ እየተጨነቅሁም እንደለመንኩት አውቆ ካሁን ጀምሮ የምገልፅልህን ፃፍ አለኝ" አለ።

6. እንዲህም አለ "ከዚያም ወደደብረዘይት አወጣኝ ጌታችን መድሐኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ወደሰማይ ካረገበት ቦታም

ጴጥሮስ ዓቢየ ብካየ ወዓተበኒ በትእምርተ መስቀል ወይቤ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ርድአኒ በዕንተ አዚአከ ከመእንግር ለዝ ረድእ ምሥጢራቲከ፡፡

7. ወእምዝ ሰገደ ዲበምድር ፯ ጊዜ ወአነሂ ምስሌሁ ሰገድኩ ወበድሕሬሁ ተመይጠ ኀቤየ ወናሁ ርኢኩ የአውደ ዓቢይ ብርሃን ከመብርሃነ ፀሐይ ወይወፅእ እምአፉሁ አምሳለነደ እሳት ወመፅአ ላእሌየ ዓቢይ ፍርሐት ወድንጋጼ ወወደቁ በገፅየ ዲበምድር፡፡

8. ወአሐዘኒ ቅዱስ ጴጥሮስ እዴየ ወአንስአኒ ወይቤለኒ ኢትፍራሕ ኦ ወልድየ ቀሌሚንጦስ ሰበርኢከ ተአምራተ ወመንክራተ ዘርኢነ በኀበእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ደንገፅከ ወኢክህልከ ተናግሮ እምብዝሐፍርሐት ወለነኒ አልቦ ዘተከሠተ ዘእንበለ ሕዳጥ እምእበየግርማሁ፡፡

9. ወይቤለኒ ዕቀብ ኵሎ ዘእነግረከ እስመናሁ ይመፅኡ እምድሕሬየ ካልአን እለኢየአምኑ በቃልየ ወበቃልከኒ ወአዲ ኢየአምኑ በስብከቶሙ ለኵሎሙ አርድእት፡፡

አቆመኝ ታላቅ ልቅሶም እያለቀሰ እኔን በትእምርተ መስቀል ባረከኝ ጌታዬ ኢየሱስ ክርስቶስ ሆይ በኀይልህ ዕናት ምሥጢሮችህን ለዚህ የኔተማሪ ቀሌሚንጦስ እገልፅለት ዘንድ ርዳኝ" አለው፡፡

7. ቅዱስ ጴጥሮስ ተናግሮ ሥግደቱን ቀጠለ አርባጊዜ ሳያቋርጥ ሰገደ እኔም ከሱጋር ሰገድኩ እሱ አርባ ጊዜ ከሰገደ በኋላ ፊቱን ወደኔ አዞረ፡፡ በዚህ ጊዜ ትልቅ ብርሃን ከላዩ ላይ ሲወጣ ተመለከትኩ ከአፉም የእሳት ነበልባል የመሰለ ነገር ሲወጣ አየሁ፡፡ በዚህ ጊዜ ፍርሃትና ድንጋጤ አደረብኝና በፊቴ ወደምድር ወደቅሁ፡፡

8. ቅዱስ ጴጥሮስ እጄን ይዞ ከወደቅሁበት አስነሳኝ፡፡ ልጄ ቀሌሚንጦስ ሆይ አትፍራ በማለትም አፅናናኝ እንዲህም አለኝ ከጌታችን መድሐኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ዘንድ ያየነውን ድንቅ ተአምር ባየህ ጊዜ ደነገጥክ ልትናገርም አልቻልክም ብዙ ፍርሀት ተሰምቶሃልና ከባድ ድንጋጤም አድሮብሃልና ለኛ ለተማሪዎቹም ከግርማው አስፈሪነት የተነሳ የምንችለውን ያህል ጥቂት ምሥጢርን ነው የገለፀልን፡፡

9. እንዲህም አለኝ "የምነግርህን ሁሉ በጥንቃቄ ጠብቅ እኔ የምናገረውን ሁሉ የማይቀበሉ በኋላ ዘመን ይመጣሉ አንተ የምትሠጠውንም ትምህርት የማይቀበሉ ይመጣሉ፡፡ ዳግመኛም የሐዋርያትን ሁላቸውን ትምህርት የማይቀበሉ ሰዎች ይመጣሉ፡፡

10. ወካዕበ ይቤለኒ ለቡኬ ኦ ወልድየ ቀሌሚንጦስ ከመሶበፈቀደ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ይዕርግ ውስተ ሰማይ አዕረገኒ ውስተ ዝንቱ ደብር ቅዱስ ወይቤለኒ ኦ ጴጥሮስ ኢትፍራሕ እስመአነ መሠረታ ለቤተክርስቲያን ወላእሌከ ሐነፅክዋ፡፡

11. ወሰገድኩ ቅዱሜሁ ወእቤ ዘከመ እፎ ፈጠርኮሙ ለሰማያት ወምድር ወእምቅድመ ትፍጥሮሙ በአይ መካን ሀሎከ ወእፎ ውእቱ መካን ዘይሴብሐከ እስመአልቦ ዘፈጠርከ ቀዳሚ ወኢምንተኒ በዲበምንት ነበረ መንግሥትከ እስመአልቦ መካን ዘያገምሮ፡፡ ወእፎ ኮንከ ለሊከ፡፡

12. ወአውስአኒ እግዚእየ ወይቤለኒ ኦ ጴጥሮስ ናሁ ዕፁብ ነገረ ተስእልከኒ ዘኢይክል ጥበበሰብእ አእምሮቶ ወባሕቱ ሶበአእመርኩ ትፈቅድ ታእምር ዘንተ ምሥጢረ አነ እከሥት ለከ ኵሎ፡፡

13. ወይቤለኒ አነ ውእቱ መካን ዘያገምሮ ለኵሉ ነበርኩ ዲበመንበረ ስብሐትየ በብዕለ ፀጋየ ወህለወ አብ ብየ ይሴብሀ ወአንስ በመንፈስ እትወደስ አልቦ ዘቀደመ እምኔነ ወኢማእከሌነ ኢቀዳሚ ወኢደሐሪ አልብነ ጥንተ

10. ዳግመኛም እንዲህ አለኝ "ልጄ ቀሌሚንጦስ ሆይ ልብ ብለህ አስተውል ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ወደሰማያት ያርግ ዘንድ በወደደ ጊዜ ወደዚሁ አመጣን ወደዚሁ ተራራም እንድንወጣ አደረገ በዚህ ጊዜ ከሌሎቹ ሐዋርያት ለይቶ ጴጥሮስ ሆይ አትፍራ እኔ የቤተክርስቲያን መሠረት ነኝና ቤተክርስቲያንን ካንተ ላይ እሠራታለሁ አለኝ"፡፡

11. እኔም ከፊቱ ሰገድኩ ሰማዮችንና ምድርን እንዴት ፈጠርካቸው ሳትፈጥራቸውስ የኖርክበት ቦታ ምን ይባላል እሱስ የት ይገኛል፡፡ የምትመሰገንበትስ ቦታ የት ይገኝ ነበር ምክንያቱም ከዚያ በፊት የፈጠርከው ነገር ለኛ አይታወቀንምና መንግሥትነትህስ በምን አማኝነት ይታወቅ ነበር ያንተን መንግሥት ሊሸከም የሚችል ቦታ የለምና አንተሳ እንዴት ትገለጥ ነበር፡፡

12. ጌታዬም መለሰልኝ እንዲህም አለኝ፡፡ "ጴጥሮስ ሆይ አሁን አስደናቂ ነገርን ጠየቅኸኝ የጠየቅኸውም ጥያቄ የሰው ልቡና ሊሸከመው የማይችል ነው፡፡ ነገር ግን ይህን ምሥጢር ለማወቅ እንደምትፈልግ ስላወቅሁ ለማወቅ የምትችለውን ሁሉ እገልፅልሃለሁ፡፡

13. ቦታ እኔ ነኝ ሁሉንም ችየ የምኖር እኔ ነኝ በምሥጋና መንበሬ ላይ ነበርኩ በፀጋየ ኃብት ነበርኩ አብ በኔ ዘንድ አለ በኔም ዘንድ መንፈስ ቅዱስ አለ ከኛ ዘንድ የመቅደምና ወደኋላ ማለት የለም ከመካከላችንም ፊተኛና ኋለኛ ተብሎ

ወኢተፍፃሜት።

14. ሕላዌነ ውስተኩሉ ወዕበየ ሐይልነ ወዘእምታሕቴነ እምፍጥረትነ ውእቱ ወአልብነ ኑኅ ወግድም ናገምር ኩሎ ወኩሉ ኢየአምረነ ወኢምንተኒ መልእልቴነ እስመመልእልተ ኩሉ ንሕነ ወአልቦ ወኢምንተኒ እምታሕቴነ እስመለኩሉ የአውዶ ዕበየ ሐይልነ።

15. አልብነ ይምን ወኢፅግም ወአልብነ ውሳጤ ወአፍአ እስመንሕነ አፍአ ወውሣጤ ስብሐቲነ ወብዕለፀጋነ እምኀቤነ ውእቱ ወኢኮነ እምባእድ አብሰ ጽድቅ ወርትእ ወአነኒ ሣህል ወምሕረት ወመንፈስ ሐይል ወጥበብ።

16. አልቦ ሰማይ ዘያገምረነ ወኢምድር ዘይፀውረነ ወሀበሀለውነ ኢንትዌለጥ እምግብር ውስተግብር ወኢንትመየጥ እመካን ውስተመካን ወኢይሬእየነ ዓይን ወጥበቢሁ ለሰብእ ኢይክል አእምሮተነ።

17. ወአልቦ ላእሌነ ተውሳክ ወኢሕፀት አብ አእምሮ ወአነ ሥምረት ወመንፈስቅዱስ ሐይል ወንሕነሰ ኢኮነ ብዙኃነ ወኢንትፈለጥ ዘዚአነ ኢይረክበነ ቡአዴ ወኢሙስና ወኩሎ ፈጠረ አብ ብየ ወበመንፈስቅዱስ ተፍፃሜቱ።

18. አብ ነቢብ ውእቱ ወአነ ቃል ወመንፈስቅዱስ ሕይወት

የሚነገርለት የለም መጀመርያና መጨረሻም የለንም።

14. የኛ ህላዌ የኛ መገኘት በሁሉ ዘንድ ነው የኃይላችንም ታላቅነት በሁሉ ይገኛል እ የፈጠርነው ሁሉ ከኛ የበታች ሁኖ ይኖራል ርዝመታችንና ስፋታችን በሰው አእምሮ አይገመትም ሁሉን እንችላለን ሁሉ ግን ማንነታችንን ሊረዳ አይችልም እኛ ከሁሉ በላይ ነንና የሐይላችንም ታላቅነት ሁሉንም ይዟልና።

15. ግራና ቀኝ የለንም ውስጥና ውጭም በኛ ዘንድ የለም ውጭ እኛ ነን ውስጥም እኛ ነን ምስጋናችንና የፀጋችን ኃብት ከኛ ዘንድ ነው። ከባዕድ የሚያስፈልገን ነገር ፈፅሞ የለም አብ እውነተኛና ትክክለኛ ነው እኔም ይቅርታና ምሕረት ነኝ መንፈስቅዱስ ኃይልና ጥበብ ነው።

16. እኛን መሸከም የሚቻለው ሰማይ የለም ምድርም የለም። ከግብር ወደግብር መለዋወጥ በኛ የለም ከቦታ ወደቦታም እንመላለስም የሰው ዓይን እኛን አያይም ሰውም በመራቀቅና በመመራመር እኛን ሊያውቅ አይችልም።

17. በኛ ዘንድ ጭማሪም ሆነ ሕፀት የለም አብ አእምሮ ነው እኔም ሥምረት ነኝ መንፈስ ቅዱስም ሐይል ነው እኛ ብዙዎች አይደለንም አንለያይምም ልዩነት አያገኘንም ጥፋትም አያገኘንም አብ በኔ ሁሉን ፈጠረ በመንፈስ ቅዱስም ተፈፀመ።

18. አብ ነቢብ ነው እኔም ቃል ነኝ መንፈስቅዱስ ደግሞ ሕይወት

ውእቱ ወአልቦ ዘይትማሰለነ እስመመልእልተ አምሳል ንሕነ ወአልቦ ዘይከውን ከማነ እስመላዕ[ከ]ሉ ንሕነ አቡየ እሳት ውእቱ ወአነ ብርሃኑ ወመንፈስቅዱስ ዋዕዩ አቡየ ፀሐይ ወአነ ብርሃኑ ወመንፈስ ቅዱስ ዋእዩ።

19. አቡየ ማይ ወአነ ጣዕሙ ወመንፈስ ቅዱስ ሕይወት አቡየ ክብር ወአነ ብዕል ወመንፈስቅዱስ ጸጋ ዘእንበሌነሰ አልቦ ፍጥረት እስመ እምቅድመ ሰማያት ሀሉኩ ምስለ አብ አቡየ ግርማ ወአነ ጸጋ ወመንፈስ ቅዱስ ተፍፃሜት።

20. አነ በአብ፣ ወመንፈስ ቅዱስ ወአብ ብየ አቡየ ጥበብ ወአነ ቃል ወመንፈስ ቅዱስ ድምፅ ንሕነ ውእቱ ዘፈጠርነ በጥበብነ ወቀዳምያን ንሕነ ወአልብነ ጥንት ወኢተፍፃሜት።

21. ወኢይትዓወቅ መዋዕሊነ እስመ እምቅድመመዋዕል ወአዝማን ንሕነ ኢይቀርብ ኀቤነ ወኢምንትኒ ወኢይክል ሕሊና ሰብእ ወኢዘመላእክት አእምሮ እስመንሕነ መልዕልተኩሉ ሕሊናት። ወኮነ ስብሐቲነ እምኀቤነ።

22. ወንሕነ ዘእንበለጥንት ወኢተፍፃሜት ፈቀድነ በብዙሕ ፍቅርነ ንፍጥሮ ለዓለም ከመይትዓወቅ መንግሥትነ ወምልክናነ ወዕበየኃይልነ ወብዕለክብርነ ይቤለነ አብ ሊተ

ነው የሚመሳሰለን የለም እኛ ከመመሳሰል በላይ ነንና እንደኛ የሚሆን የለም እኛ ከሁሉ በላይ ነንና አባቴ እሳት ነው ብርሃኑም እኔ ነኝ ሙቀቱም መንፈስ ቅዱስ ነው አባቴ ፀሐይ ነው ብርሃኑም እኔ ነኝ ሙቀቱም መንፈስቅዱስ ነው።

19. አባቴ ውሃ ነው እኔም ጣዕሙ ነኝ። መንፈስ ቅዱስም ሕይወት ነው አባቴ ክብር ነው እኔም ክብር ነኝ መንፈስ ቅዱስም ጸጋ ነው። ከኛ ውጪ ፍጥረት የለም። ሰማያት ሳይፈጠሩ እኔ ከአብ ጋር ነበርኩ አባቴ ግርማ ነው እኔ ደግሞ ጸጋ ነኝ መንፈስ ቅዱስ ፍፃሜ ነው።

20. እኔ በአብ መንፈስ ቅዱስ በአብና በኔ አባቴ ጥበብ ነው እኔም ቃል ነኝ መንፈስ ቅዱስ ደግሞ የቃል ድምፅ ነው። እኛ ነን በጥበባችን ሁሉን የፈጠርን ቀዳሚዎችም እኛ ነን መጀመርያና መጨረሻም የለንም።

21. ዘመናችን በፍጡራን ዘንድ አይታወቅም ከዘመንና ከአዝማን በፊት እኛ ነን። ከኛ ዘንድ የሚቀርብ የለም የሰው ሕሊናና የመላእክት አእምሮ ሊደርስብን አይችልም። እኛ ከሁሉ በላይ ነን። ከሕሊናዎችም በላይ ነው ምስጋናችንም ከራሳችን ነው።

22. እኛ መጀመርያና መጨረሻ የለንም ከፍቅራችን ብዛት የተነሳ ዓለምን እንፈጥር ዘንድ ወደድን ይህም መንግሥታችን ይታወቅ ዘንድ መላኬነታችንና አቸናፊነታችንም ይታወቅ

ወለመንፈስቅዱስ ንፍጥሮሙ ለእሳት ወለማያት ወለነፋሳት ወለባእዳን፡፡

23. ወፈጠርኖሙ እሞትካት ለሰማያት ቱሱሐን ምስለማያት ወምድርኒ ሀለወት ምስለማይ እንዘኢትከውን ፅንዕተ ፍፁመ ወኩሎሙ እሙንቱ ወእምዝ ፈጠርነ ንፁሐነ ሰማያተ ከመይኩን ምግባሪነ ላእሌሆሙ ወነበርነ ህየ፡፡

24. ወኢይክል ሕሊና ጥበብከ ኦ ጴጥሮስ እምዝንቱ ነገር ዘሰማዕከ ምሥጢረ ሥላሴ ወእምዝ ነሣእነ ፅሩያነ ማያተ ወፈጠርነ እምኔሆሙ ፫ ሰማያተ ብሩሀነ ወልዑላነ ዘእምታሕተ ሰማይ ዘምግባሪነ ላእሌሆሙ ወብርሃነ ዘፈጠርነ እንዘሀሉነ ላዕላይ፡፡

25. ሕልው ውእቱ ውስተሰማያት ዘእንበለውላጤ ወኢማሕለቅት እስመምግባኢሁ ለኩሉ ኀቤነ ወኩሉ ሀሎ በእራሕነ ወሶበፈፀምነ ፈጢሮቶሙ ለ፯ ሰማያት በቅፅበት ፈጠርነ ካልአ ፯ተ በቃል፡፡

26. ወእምዝ ረሰይነ ውስቶቶሙ በጥበብነ ዘአልቦ ትልቊ ወአልቦ ካልእ ዘየአምሮ ዘእንበሌነ ወአስተጋባእናሆሙ ለኩሎሙ ማያት ዘእምታሕተሰማያት ዘስሙ ፋሌክ

ዘንድ ብዕላችንና የኃይላችን ከፍታም ይታወቅ ዘንድ አብ እኔና መንፈስ ቅዱስ እሳትን ውሆችንና ነፋሶችን እንፍጠራቸው አልን፡፡

23. እኛም ፈጠርናቸው ከዚያ በፊት ሰማዮች ከውሆች ጋር ተቀላቅለው ነበር ምድርም ከውሃ ጋር ነበረች የፀናችም አልነበረችም ሁሉም በዚሁ መልክ ነበሩ፡፡ ከዚህ ቀጥሎ ሥራችን ከነሱ ላይ ይሆን ዘንድ ሰማዮችን ፈጠርን በነሱ ላይም እንኖራለን፡፡

24. ጴጥሮስ ሆይ የጥበብህ ህሊና ስለሰማኸው ምሥጢረ ሥላሴ ሊሸከመው አይችልም፡፡ ይኸውና እኛ የጠሩ ውሆችን ፈጠርን ከነሱም ሦስት ሰማዮችን ፈጠርን፡፡ ሰማዮቹ ብሩሃን ናቸው ልዑላንም ናቸው፡፡ የኛ ሥራ በነሱ ላይ ነው የፈጠርነው ብርሃንም ላይኛው ነው፡፡

25. ብርሃኑ በሰማዮች ያለ ነው፡፡ ይህም ብርሃን አያልቅም አይለወጥምም የሁሉም መድረሻና መነሻ እኛ ነን ሁሉም የሚኖረው በመዳፋችን ነው ሰባቱ ሰማያትን ፈጥረን ከጨረስን በኋላ በቅፅበት ሌሎች ሰባት ሰማዮችን ፈጠርን የፈጠርነውም በቃላችን ነው፡፡

26. በነሱ ላይም በጥበባችን ሥፍር ቁጥር የሌላቸውን ሌሎች ፈጠርን፡፡ ከኛም በቀር ማንም አያውቃቸውም፡፡ ውሆችንም ሁሉ አንድ ላይ ሰበሰብናቸው የሰበሰብናቸውም ከሰማያት

ውስተ ፩ መካን ዘየአውዶ ለኩሉ ዓለም ወፈጠርነ ኩሎ ዘዘዚአሁ።

27\. ወፈጠርነ ኩሎ ዘዘዚአሁ ፍጥረተ ወፈጠርናሆሙ ለመላእክት ፱ ዘመድ ዘዘዚአሆሙ አርአያሆሙ በበፆታሆሙ አርአያሆሙ ከመይርአዮ ፩ለካልኡ ወኩሎሙ ወቦ እመላእክት ዘቦ ብዙሕ ዓዕይንቲሁ ወዘብዙሕ ገፁ። ወቦ እምኔሆሙ ዘኩለንታሁ እሳት ዘይነድድ።

28\. ወቦ እምኔሆሙ መንፈስ ባሕቲቱ ወቦ እምኔሆሙ ዘውእቱ መንፈስ ወእሳት ወኩሎሙ ይዜምሩ ወይሴብሐ በቃል ዘኢያረምም እምዕራገመላእክት እስከካልእ ምዕራገ መላእክት የአክል ከመ ማእከለሰማይ ወምድር ዘትሬኢ።

29\. ትልቆሙ ለእሙንቱ መላእክት እለቦሙ ክንፍ ዘኢያረምሙ እምስብሐቲነ ፻፻ ወአእላፋት ወትእልፊተ አእላፋት ሱራፌል ወኪሩቤል ይሴብሁነ በቃል ዘኢያረምም

30\. ወኩሎሙ በበፆታሆሙ ወበውስተ ፫ አብያተክርስቲያናት ዘብርሃን ወእሳት ወፈጠርናሃ ለኢየሩሳሌም ሰማያዊት መልዕልተማይ ዘመልእልተ ሳልስ ሰማይ።

በታች ነው። ይህም ውሆች የተሰበሰቡበት ቦታ ፋሲክ ይባላል ይህም አንድ ቦታ ሁኖ ዓለምን ሁሉ ይዞራል።

27\. ብዙ የተለያዩ ነገሮችን ፈጠርን ዘጠኙንም ነገደመላእክት ፈጠርን የነሱም መልክ ይለያያል በየነገዳቸው ሁሉ መልካቸው ይለያያል። አንዱ ሌላውን ያየዋል ሁላቸውም በየነገዳቸው ይለያያሉ። ከመላእክት መካከል ብዙ ዓይኖች ያሉት አለ። ፊቱም ብዙ የሆነ አለ ሁለመናውም የሚነድ እሳት ሁኖ የተፈጠረ አለ።

28\. መንፈስ ብቻ ሁኖም ከነሱ መካከል አለ። መንፈስና እሳት በመሆንም የተፈጠሩ አሉ ነገርግን ሁሉም ይዘምራሉ ያለዕረፍትም በማያቋርጥ ያመሰግናሉ ካንዱ የመላክት ማረጊያ ወደሌላው የመላእክት መገኛ የምትመለከተውን የሰማይና የምድር ርቀት ያህላል።

29\. የነዚህ መላእክት ቁጥር እልፈ አዕላፋት ከዚያም የእጥፍ እጥፍ ነው እነዚህ እኛን በማመስገን ይኖራሉ ዕረፍት የላቸውም። ሱራፌልና ኪሩቤልም በየፊናቸው ያመሠግኑናል ዕረፍትም የላቸውም።

30\. ሁሉም በየወገናቸው በሦስቱ የብርሃን፣ የእሳት አብያተ ክርስቲያናት ላይ ይገኛሉ ኢየሩሳሌም ሰማያዊትንም ከሰማይ በላይ ከሚገኘው ውሃ በላይ ፈጠርናት እሷ ከሦስቱ ሰማያት በላይ ትገኛለች።

31. ወትጌልላ ለኢየሩሳሌም ምድራዊት ወሕንፀታ ዘብርሃን ወአእማዲሃ ዘእሳት ሥርግዋን በዓቢይ ግርማ ወቤተመቅደስነ እሳት ዘይነድድ ወታቦት ዘእምብርሃን ዘኢይክል ወኢመኑሂ ርእዮቶ። ወኩለንታሃ ብርሃን ወፀዳል ወክልልት በግርማ።

32. ወክልልት በግርማ ወቅድስት ወየዓውዳ ብርሃን ወብዕለ ፀጋ ወይወፅእ እምኔሃ ዜና መዓዛ ሠናይ ዘኢይከውን፡ ከማሁ በውስተኩሉ ዓለም።

33. ለብርሃን ዘውስቴታ ኢይረክቦ ጽልመት ወኢይትዓወቅ ኑኃ ወግድማ ወኢቆማ ወየሐድር ኀይልነ ውስቴታ እምሥራቅ።

34. ወናሁ እከሥትለከ ኦ ጴጥሮስ ዘዓይን ኢርእየ ወእዝን ኢሰምአ ውስተ ልበ ሰብእ ዘኢተሐለየ ወረሠይነ ምግባረነ እምብርሃን ወእሳት ወግርማ ወ፬ እንስሳ ይፀውርዎ እለበሙ ብዙኀን ዓዕይንት።

35. ወይወፅእ እምአፉሆሙ አምሳለ ነደእሳት ወእሙንቱ ገጸ ሰብእ ወገጸእንስሳ ገጸንሥር ወገጸ አንበሳ ወይቀውሙ ፬ቲሆሙ በየማኑ ወበፀጋሙ ወክነፊሆሙ ለኩሎሙ

31. ኢየሩሳሌም ምድራዊትን ትጋርዳታለች ሥራዋም ከብርሃንና ከፀዳል ነው ምሰሶዎቿ ከእሳት ናቸው። እሷ የቆመችባቸው ምሰሶዎች በታላቅ ግርማ ያሸበረቁ ናቸው ቤተመቅደሷም የሚነድ እሳት ነው በውስጧ ያለው ታቦት ከብርሃን የተሠራ ሁኖ ማንም ሊመለከተው የማይችል ነው። የታቦቷ ሁለንትና ግርማ ፀዳልና ብርሃን ነው።

32. ሰማያዊቷ ኢየሩሳሌም በግርማ የታጀበች ቅድስት ናት የፀጋ ብዕልና ብርሃን ዙሪዋታል ከሷ የሚወጣው አእምሮን የሚመስጥ ሽቶ በዓለም ሁሉ ሊገኝ የማይችል ግሩም ነው።

33. በኢየሩሳሌም ሰማያዊት ላይ ያለው ብርሃን ዕልመት አያገኘውም የሷንም ጉድን ቁመትና አቀማመጥ ፊዕሞ በፍጡራን ሊታወቅ አይችልም።

34. ጴጥሮስ ሆይ እነሆ ጆሮ ያልሰማውንና ዓይን ያላየውን በሰው ልቡናም የማይታሰበውን ልገልፅልህ ነው እኛ (ሦስቱ አካላት) ከግርማ፣ ከእሳትና ከብርሃን ሥራችንን ሠራን ይህ የሠራነው ሥራ ከብርሃን ሥራችንን ሠራን ያህም የሠራነው ሥራ ከብርሃን ከእሳት አራቱ እንስሳ ይሸከሙታል። እነዚህ እንስሳት ብዙ ዓይኖች ያሉዋቸው ናቸው።

35. ከአፋቸው የነደእሳት አምሳል ይወጣል እነሱ የሰው ፊት የእንስሳፊት የንሥር ፊትና የአንበሳ ፊት ናቸው። አራታቸው በግራና በቀኝ ይቆማሉ የሁላቸው ክንፍ የሚነድ

እሳት ዘይነድድ፡፡ ወእምታሕቴሆሙ መንኩራኩር ዘእሳት፡፡

36. ላእለ፪ ባሕር ፩ዘእሳት ወካልኡ ዘየዓቢ ዘነፋስ ወእምታሕቴሁ ባሕር ይውኀዝ ውስተ ገነተ ትፍሥሕት፡፡

37. ዜና መዓዛ ሠናይ ዘይዔኑ እምኩሉ ርኄእፈው ወነበኀለወ ባሕር ዘእሳት፣ ዘነፋስ ህየ ይውኀዝ ባሕር ብርሃን ወኢይትአወቅ ጥንቱ ወኢተፍፃሜቱ ወኢየአምሮ ወኢመኑሂ እምኩሉ ዘበሰማይ ወዘደምድር፡፡

እምኀበይወፅእ ኀበ የሐውር ወነበይበፅሕ ወየዓውዶ ዓቢይ ጽልመት፡፡ ዘአልበ ብርሃን ወኩሎሙ ኢይትመሰሉ በብርሃን፡፡

38. ኦ ጴጥሮስ ለነሰ ስብሐቲነ እምነቤነ ውእቱ ዘእንበለ ዓርምሞ ወዘእንበለ ተፍፃሜት ወኢማሕለቅት ወኢነሐፅፅ ተወስኮ ኢንፈቅድ ንሕነ፡፡ ንሕነ ውእቱ ቀደምት ወደሐርት ወኩሉ ውስተእራኅነ ወረሰይናሆሙ ለደመናት ታሕተ መከየደ እገሪነ፡፡

39. ወአዘዝናሆሙ ለሱራፌል ወኪሩቤል ይኪዱ መታክፍቲሆሙ ለነፋሳት ወንኜንፅራ ለምድር ወንሬስያ ከመትርአድ ወኢይክሉ ዓዕይንተመላእክት ይርአዩነ አላ

እሳት ነው ከነሱ ቀጥሎ ደግሞ ከእሳት የተሠራ አስፈሪ መንኩራኩር ይገኛል፡፡

36. በሁለት ባሕሮች ላይ አንዱ የእሳት ሌላው የነፋስ የሆኑ ናቸው፡፡ (መንኩራኩሮቹ) ከበታቹ እየተነሳም ወደገነት የሚፈስ ባህር አለ፡፡

37. ከመልካም ሽቶ ሁሉ የበለጠ መልካም ሽቶ በዚያ አለ የእሳት ባሕር ካለበትም ቦታው ነፋሻማ ይሆናል ወደዚሁም ከብርሃን የሚፈልቀውና መጀመርያው የማይታወቅ መጨረሻውም የማይታወቅ ነው፡፡ ከሰማይ ካለው ሁሉም የዚህን አመጣጥ የሚያውቅ የለም፡፡ በምድር ያለውም የዚሁን መነሻ አያውቅም የሚወጣበትና የሚደርስበትም አይታወቅም ትልቅ ድቅድቅ ጨለማም ይከበዋል ይህ ድቅድቅ ጨለማ ከብርሃን የተለየ ቦታ ነው ከብርሃን የማይማሳሰሉ ሁሉ ከዚያ አሉ፡፡

38. ጴጥሮስ ሆይ እኛስ ምስጋናችን ከኛ ዘንድ ነው ምስጋናችንም አይቋረጥም መጨረሻም የለውም ፍፃሜም የለውም እኛ ከሶስትነት አናንስም ጭማሪም አንፈቅድም ቀደምት እኛ ነን ኋለኞችም እኛ ነን ማነኛውም ነገር ሁሉ በመዳፋችን ነው፡፡ ደመናትንም ከእግራችን መረገጫ በታች እንዲሆኑ አደረግን፡፡

39. ሱራፌልንና ኪሩቤልን የነፋሳትን ትክሻዎች ይረግጡ ዘንድ አዘዝናቸው ምድርንም እንመለከታታለን እንድትንቀጠቀጥም እናደርጋለን የመላእክት ዓይኖች እኛን መመልከት አይችሉም

ባሕቱ ይሴብሑነ ወይቄድሱነ ንሕነ ውእቱ ፪ ሌቃውንተ ዘ፪ መዓርጋተ መላእክት ዘረሰይነ።

40. ወለእሉ አዘዝናሆሙ ይዑዱ ማሕደረነ እስመ ፩ሊቅ ሚካኤል ዘውእቱ መልአከ መዓት ወቀትል ወስመካልኡ ገብርኤል ላእከ ወዜናዊ ዳህን ወሰላም።

41. ወአስማቲሆሙ ለካልአን ፪ ሊቃውንት ሱሩያል ወሩፋኤል ወእሙንቱ ላእካነዜንዎ። ወገብርኤል ሀለወ ውስተ ሰማይ ወሠራዊቱ የዓውዱ ማሕደረ ብርሃን ወመልዕልተ ኩሉ ንሕነ።

42. ወለእመቦ ዘፈቀድነ ንገብር አልቦ ዘይከልአነ እምኩሉ ፍጥረት ወኢየአምረነ ሕሊና ጥበቢሆሙ ለመላእክት ወኢይለክፉ አዕይንት ወኢንትፈለጥ ዘዘዚአነ ምሕረትነ ተአትቶ ለመዓትነ ወሣህልነ ታቈርሮ ለመዓትነ ወለኩነኔ ኢንሜጡ በከመፍትው ዘእንበለ በፍትሕ ወበሣሕል ወበ ምሕረት።

43. ንሕነ ንፈጥሮ ለኩሉ ዘእንበለ ፃማ ናቀርቦ ለርሁቅ ወናርሕቆ ለቅሩብ ንሬእዮ ወናርሕቆ ለቅሩብ ንሬእዮ ለኩሉ ወአልቦ ዘይሬእየነ ወውስተኩሉ ንሕነ ወንገብር

ሥራቸው እኛን ማመስገን ብቻ ነው ያመሰግኑናልም የመላእክት ዓለቅነትን በሁለት መዓርጋት መላእክትን የፈጠርን እኛ ነን።

40. እነዚህም መንበራችንን እንዲዞሩ አዘዝናቸው። አንደኛው አለቃ ሚካኤል ነው እሱም የመዓት መልአክ ነው ሁለተኛው ደግሞ ገብርኤል ነው ገብርኤል መልእክተኛ፣ የደኅንነትንና የሰላምን ብሥራት ነጋሪ ነው።

41. የሁለቱ ሌሎቹ አለቆች ስም ሱሩያልና ሩፋኤል ይባላል። እነሱም የዜና መልእክተኞች ናቸው ገብርኤል በሰማይ ውስጥ ይኖራል። የሱ ሠራዊት ደግሞ የብርሃንን ማሕደር ይዞራሉ እኛም ከሁሉ በላይ ነን።

42. የፈለግነውን ለመሥራት ካቀድን የሚከለክለን የለም ከፍጥረት ሁሉ ሊቃወመን የሚችል ማንም የለም የመላእክት ጥበብ ሕሊናም አያውቀንም ዓይኖች አይነኩንም እያንዳንዳችን አንለያይም ቁጣችንን ምሕረታችን ታስወግደዋለች። ኩነኔ ይቅርባይነታችንም መዓታችንን ታቀዘቅዘዋለች። ኩነኔ የሚገባው ቢኖርም በትክክለኛው ፍርዳችን በምሕረትና በይቅርታ እንጐበኘዋለን እንጂ አናጠፋውም።

43. እኛ ሁሉንም እንፈጥራለን የምንፈጥረውም ያለድካም ነው የራቀውን እናቀርባለን የቀረበውን እናርቃለን ሁሉን እናያለን እኛን ግን የሚያየን የለም በሁሉም ዘንድ እኛው ነኝ

ንሕነ ኃይለ ወመድኀኒተ ወኀይልነ ሥሉጥ ለኩሉ ዘፈጠርነ ወእኮ ዘንፅሕቅ ስብሐተ እምንበዘፈጠርነ ስብሐቲነሰ እምነቤነውእቱ ወኩሉ ኀይል ዘእምኃይልነ ውእቱ።

44. ወጸጋነ ይፈደፍድ እምኩሉ ጸጋ ወክብርነ የዓቢ እምኩሉ ክብር።

45. ለቡ እንከ ጴጥሮስ ወአእምር እምግብርየ ከመአነ ውእቱ እግዚአብሔር እስመኩሉ ኬንያ ይትዓወቅ በጥበቢሁ።

46. ወሰበ ተናገረኒ እግዚእየ ወአምላኪየ ወመድኀንየ ኢየሱስ ክርስቶስ በእንተፍጥረተ ሰማያት ወምድር ወበእንተፍጥረተማያት ወነፋሳት አእመርኩ ወጠየቁ ከመእግዚእ ፈጣሬኩሉ።

47. ወካዕበ ይቤለኒ አእምርአ ጴጥሮስ ከመበኀቤየ ይከውን ክረምት ወሐጋይ እስመአነ ውእቱ አምላከ ክረምት ወሐጋይ አነ ምስለአብ ወመንፈስ ቅዱስ ዘእንበለፍልጠት።

48. ወንሕነ ናወርድ ዝናማተ ወናረውያ ለምድር ወንሬስያ ለባሕር የብሰ ወለየብስ ባሕረ ወለአፍላግ የብሰ ወንፌኑ ንስቲተ ነፋሰ እምባሕረ ነፋሳት ወያመዘብሩ ብዙሐነ አሕጉረ። ወነሐንፅ አድባረ ወአውግረ ነዋሐተ

ሐይልንና መድኀኒትን የምንሠጥ እኛ ነን ኃይላችን ከሁሉም በላይ የኛ ኃይል የሠለጠነ ነው ከፈጠርነው ፍጡር ምስጋናም አንሻም ምስጋናችንስ ከኛው ነው ኃይልም ሁሉ ከኃይላችን ነው።

44. ጸጋችን ከጸጋ ሁሉ ይበልጣል ክብራችንም ከክብር ሁሉ ይበልጣል።

45. ጴጥሮስ ሆይ ልብ በል አስተውልም ከሥራየም ተረዳ እኔ እግዚአብሔር እንደሆንኩም እወቅ ብልሐተኛ ሁሉ በጥበቡ ይቃወቃልና።

46. ጌታችንና መድሐኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ስለሰማያትና ስለምድር አፈጣጠርና ስለነፋሳትና ስለውሆች አፈጣጠር በነገረኝ ጊዜ ጌታችን ሁሉን የፈጠረ እንደሆነ አወቅሁ ተረዳሁም።

47. ደግሞም ጴጥሮስ ሆይ አስተውል አለኝና ክረምትና በጋ በኔ ይሆናሉ የክረምትና የበጋ አምላክ እኔ ነኝና እኔ ከአብ ጋርና ከመንፈስ ቅዱስ ጋር ያለመለየት በፍፁም ተዋህዶ እኖራለሁ መለያየት በኛ ዘንድ የለም።

48. እኛ ዝናማትን እናወርዳለን ምድርንም እናጠጣታለን ባሕርን እናደርቃለን የብስንም ባሕር እናደርገዋለን ወንዞችንም እንዲደርቁ እናደርጋለን። ከነፋሳት ባሕር ትንሽ ነፋስ ብዙ አገሮችን ታጠፋለች ተራሮችንና ኰረብቶችን እንሠራለን

ወናውሕዝ አንቅዕተ ውስተአፍላግ።

49. ርኢ ኦ ጴጥሮስ ዘከመንፌኑ እሳተ እምባሕረ እሳት ዘመልእልተ ሰማያት ያውኢ ብዙኀነ በሐውርተ ወንገብር ብዙኀ ተአምራተ ወመንክራተ ዘንቱሰ ኵሉ በዕበየ ኀይልነ። ወናረግዖሙ ለማያት በውስተ ደመናት ወንፌኑ በረደ ወአስሐትያ ውስተምድር።

50. ሰቡ እንክ ጴጥሮስ ከመዝ ኵሉ ፍጥረት ዘሥጋ ወነፍስ ወፈጠርነ ትልቆሙ ለኵሎሙ ዕጸው ወታበቁል ምድር ስሒነ ሕቡረ እስመአልቦ ባእድ ዘእንበሌነ ንሕነ ፈጠርነ በቅዕበት ዘይትዓወቅ ወዘኢይትዓወቅ ዘይትገሠሥ ወዘኢይትገሠሥ ዘየሐልፍ ወዘኢየሐልፍ ወአልቦ ዘየአምር ዘንተ ኵሎ ዘእንበሌነ። ንሕነ ሰቀልኖ ለሰማይ ዘእንበለ ዓምድ ወሣረርናሃ ለምድር ዲበ ማይ ወአንበርኖሙ ለነፋሳት።

51. ኦ ጴጥሮስ ሶበ ኢ ተሠኀኩ እምማርያም ቅድስት ድንግል እምኢፈጠርክዎ ለአዳም ወኢ ለሰማያት ወኢለምድር።

52. ኦ ጴጥሮስ ሶበኢተሰባእኩ አነ እምኢተዓውቀ ብዕለ ክብርየ

ምንጮችንም ወደወንዞች እንልካለን።

49. ጴጥሮስ ሆይ ከእሳት ባሕር ነፋስን እንደምንልክ ልብ በ(ል) ይህም የእሳት ባሕር መልእልተ ሰማያት ይገኛል። ይህ(ም) ትንሽ እሳት ብዙ አገሮችን ያቃጥላል ብዙ ተአምራትንና ብዙ መንክራትን እናደርጋለን ይህንንም ሁሉ በኃይላችን ብዛት እናደርጋለን። ውሆችንም እናረጋለን ረግተው በደመናት ላይ ዝናም እንዲሆኑ እናደርጋለን በርድንና ውርጭን ወደምድር እንልካለን።

50. ጴጥሮስ ሆይ ልብ ብለህ አስተውል የነፍሥና የሥጋ ወገን ፍጥረት ሁሉ እኛ የፈጠርነው ነው። የዕፀዋትንም ቁጥር ፈጥረናል ምድር ሥሒን የተባለውንም ከዕፀዋት ጋር ባንድነት ፈጠርን ከኛ በቀር ሌላ አምላክ የለም በቅፅበት የሚታየውንና የማይታየውን ሁሉ እኛ ፈጠርን የሚዳሰስና የማይዳሰስ የሚያልፈውንና የማያልፈውን የፈጠርን እኛ ነን። ይህን ሁሉ ከኛ በቀር የሚያውቀው የለም። ሰማይን የሠቀልነው እኛ ነን ያለምሰሶ እኛ ሰቀልነው ምድርንም በውሃ ላይ እኛ ፈጠርናት ነፋሳትንም አስቀመጥናቸው።

51. ጴጥሮስ ሆይ ከቅድስት ድንግል ማርያም ዘንድ ሥጋ ለመልበስ ባልፈልግኑሮ አዳምን ሰማያትንና ምድርን ባልፈጠርኩዋቸው ነበር።

52. ጴጥሮስ ሆይ እኔ ሰው ባልሆን ኑሮ የምሥጋናየና የክብሬ

ወስብሐትየ ኦ ጴጥሮስ ሶበኢያፍቀርኩከ እምኢከሰትኩ ለከ ዘንተ ምሥጢረ ወናሁ እከሥት ለከ ሶበሰ ኢያፍቀርክዎሙ ለሰብእ እምኢያስተርአይክዎሙ በዝንቱ ሥጋ ሶበሰ ኢኮነት ዛቲ ቅድስት ድንግል እምኢፈጠርክዋ ለሄዋን።

53. ኦ ጴጥሮስ አነ እሁበከ ስእለተከ ወእከሥት ለከ ምሥጢራትየ እስመአእመርኩ ፍቅረዚአከ እምኩሉ ፍጥረት አልቦ ዘየአምር ስነመለኮትየ አልቦ ዘይሬእየኒ ዘእንበለዳእሙ ዘቦ ርትዕት ሃይማኖት ወአነሂ አስተርእዮ በስነ መለኮትየ።

54. ወእምዝ ይቤለኒ ቅዱስ ጴጥሮስ ኦ ወልድየ ቀሌሚንጦስ ሶበተናገረኒ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ዘከመዝ ነገረ ርኢክዎ ናሁ ሠፍሐ እዴሁ ውስተ ሰማይ ወምድር ወኮነ ከመጦማር ዘውስተ ክርታስ ወአስተጋብኦሙ ውስተአራሁ።

55. ወይቤለኒ ኦ ጴጥሮስ አቅርብ እዝነከ ኀበእራኀየ ወለቡ ዘንተ ወስማዕ ወቀረብኩ ኀቤሁ ወሰማዕኩ ድምፀ ብዙኃን ሰብእ

56. ወብዙኅ አውያተ ዓቢየ ወእምዝ አብፅሐኒ ውስተግሩም መካን ዘኢኮነ ውስተሰማይ ወምድር። ወይቤለኒ ኦ

ብዕል ባልታወቀ ነበር ጴጥሮስ ሆይ ባልወድህ ኑሮ ይህን ምሥጢር ባልገለፅኩልህም ነበር። እነሆ ብዙ ምሥጢርን እገልፅልሃለሁ ሰዎችንም ባልወድ ኑሮ በዚሁ በለበስኩት ሥጋ ባልተገለፅኩላቸውም ነበር እቺ ቅድስት ድንግል ማርየምን ባልመርጣት ኑር ሄዋንን ባልፈጠርኩዋት ነበር።

53. ጴጥሮስ ሆይ እኔ የለመንከውን ሁሉ እሠጥሃለሁ ምሥጢሮቼንም እገልፅልሃለሁ እንደምትወደኝ አውቃለሁና የመለኮቴን ብርሃን ከፍጡራን ሁሉ አንድም የሚያውቅ የለም የቀናች ሃይማኖት ያለችው ሰው ካልሆነ በቀር እኔን የሚያይ የለም እኔም ለሃይማኖተኛ ሰው በመለኮቴ ግርማ እታየዋለሁ።

54. ቅዱስ ጴጥሮስ ከዚህ በኋላ እንዲህ አለኝ ልጄ ቀሌሚንጦስ ሆይ ጌታችን ኢየሱስክርስቶስ በተናገረኝ ጊዜ እያየሁት ወደሰማይና ወደምድር እጆቹን ዘረጋና ሰማይና ምድርን በትንሽ ክርታስ እንደተያዘች ደብዳቤ አስመስሎ በመጠቅለል በማህል እጁ አስቀመጣቸው።

55. እንዲህም አለኝ "ጴጥሮስ ሆይ ጆሮህን ወደማሕል እጄ አቅርብ ልብ ብለህም ይህንን ስማ" እኔም ቀረብኩ የብዙዎችንም ድምፅ ሰማሁ።

56. ብዙ ጩኸትንና ፍጅትን ሰማሁ ቀጥሎ ግሩም ወደሆነ ቦታ አደረሰኝ ይህ ቦታ ከሰማይ አይደለም [illegible] አይደለም

ጴጥሮስ አይቴ ህለውከ ወእቤሎ ኢየአምር እግዚኦ።

7. ወይቤለኒ አንሥእ ዓእይንቲከ ወናሁ ርኢኩ ጠፈረብርሃን ዘውስቴቱ መንጦላዕተብርሃን ዘውሉጥ ሕብሩ ወርእየ ወደቁ በገጽየ ወእምዝ አሐዘኒ እዴየ ወአንሥአኒ ወይቤለኒ ምንተ ትሬኢ ሰማያተ ወሚመ ምድረ።

58. ወእቤሎ አልቦ ዘእሬኢ እግዚእየ ወአምላኪየ ወይቤለኒ ነፅር ታሕተ ወናሁ ርኢኩ ዓቢየ ማዕምቀ ጽልመት ዘአልቦ ጥንት ወኢተፍፃሜት ወይቤለኒ ለቡ ዘትሬኢ ወናሁ ርኢከ ሰማያተ ፀሐየ ወወርሐ ወከዋክብተ።

59. ወምድረኒ ባሕረ ወአፍላገ ዘይውሕዙ ወኩሎሙ እትዛን በእዴሁ ውስተ እራሁ አነ ጴጥሮስ ርኢኩ ዘኢኮነ በሕልም አላ በገሀድ ኢኮነ በሐሰት። ወእምድሕረዝ አግብኦሙ ለኩሎሙ ውስተመካናቲሆሙ ወኮነ ከመትካት ንነብር ውስተደብረዘይት።

60. ወካዕበ ይቤለኒ እግዚእነ ወአምላክነ ወመድኀኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ ተመየጥ ድሕሬከ ወሶበ ተመየጥኩ ርኢኩዋ ለኢየሩሳሌም ቅድስት ወይቤለኒ አእምር ከመሰማያት ወምድር ውስተ እዴየ።

እንዲህም አለኝ "ጴጥሮስ ሆይ ያለህበት ቦታ የት ነው?"

57. ደግሞም እንዲህ አለኝ ዓይኖችህን አንሳ በዚህ ጊዜ ተመለከትኩና የብርሃን መጋረጃ ያለበት የብርሃን [illegible] አየሁ ሕብሩ የተለዋወጠ ነበር እኔም አይቼ ደነገጥኩ [illegible] በኋላ እጄን ይዞ አስነሳኝ "ያየኸው ምንድር ነው [illegible] ወይም ምድር" ብሎ ጠየቀኝ።

58. ጌታየና አምላኬ ሆይ ምንም አልታየኝም አልኩት [illegible] ተመልከት አለኝ እኔም ወደታች ተመለከትኩ የ[illegible] ጥልቀት ያለውንም ጨለማ አየሁ መነሻውና [illegible] አይታወቅም "የምትመለከተውን አስተውል" ባለኝ [illegible] ሰማዮችን ከዋክብትንና ጨረቃን ተመለከትኩ።

59. ባሕርን የሚፈሱ ወንዞችን አየሁ እነዚህ ሁሉ በጌታችን [illegible] እጅ የተያዙ ናቸው። እኔ ጴጥሮስ ያየሁት ሁሉ በሕልም ያየሁት አይደለም በገሀድ እንጂ በሐሰትም አይደለም ከዚያ ጌታችን ሁሉን ካሳየኝ በኋላ ወደየቦታቸው መለሳቸው እኛም እንደነበርንበት በቀድሞው ሁኔታችን ወደደብረዘይት ተመለስን።

60. ደግሞም ጌታችንና መድሐኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ወደኋላህ ተመለስ አለኝ እኔም ወደኋላዬ ተመለስኩና ኢየሩሳሌም ሰማያዊትን አየሁዋት። እሱም ሰማያትና ምድር በእጁ እንደሆኑ እወቅ አለኝ።

61. ወኢይትአተቱ በከመርኢከ ወበጥበበመለኮትየ ፈፀምኩ ኩሎ አነ ውእቱ አምላከ አብርሃም ይስሐቅ ወያዕቆብ ምሥጢራትየ ወምሕረትየ ኢይትአወቅ ወኢይክል ልሳን ዜንዎቶ ወባህቱ እነግረከ ዘኢይክል ጥበብከ አእምሮቶ።

62. እስመወሀብኩከ መራትተ ዘመንግሥተሰማያት ዘኢይጌይልዋ አናቅጸሲኦል ታርጉ ወትዕፁ ለዘፈቀድከ። ወእምዝ ይቤለኒ አነ ቀዳማዊ ወአነ ደሃራዊ አነ እቀትል ወአነ አሐዩ አነ አሐምሞ ወእፌውስ አነ በአብ ወአነ ወበመንፈስቅዱስ ወአብ ወመንፈስቅዱስ ብየ ወአነ ዋህድ በሥላሴ።

63. ሰማይ መንበርየ ወምድር መከየደ እግርየ፣ መኑ ውእቱ ዘይቀውም ቅድሜየ አነ ፈጠርክዎ ለአዳም በአርአያየ ወበአምሳልየ ወነፋሕኩ ላእሌሁ።

64. ወረሠይኩ ላእሌሁ መንፈሰ ለባዊተ እንተኢትመውት ወኢትትዓወቅ በስን ወበአምሳል ዘመላእክት ወረሰይክዎ ከመይትቃረኖ ለዲያብሎስ ዘወድቀ እመንበሩ ዘበሰማያት።

65. ኦ ጴጥሮስ ከሰተ ለከ አብ ከመአነ ወልዱ ወአለብወከ ከመአነ ሎቱ ዋሕዱ ኦ ጴጥሮስ ናሁ ንሕነ ፈጠርነ ኤደምሃ በጊዜ ፈጠርናሆሙ ለመላእክት ወረሰይክዋ ለቤተክርስቲያን ቤተፀጋየ ወሴምኩ ውስቴታ አፍላገ

61. እንዳያሃቸው የትም አይወገዱም በመለኮቱ ጥበብ ይህን ሁሉ ፈፀምኩ። የአብርሃም ይስሐቅና ያዕቆብ አምላክ እኔ ነኝ ምሕረቴና ምስጢሬ አይታወቅም ነገር ግን ያንተ አእምሮ ሊቀበለው የማይችለውን ምሥጢር እነግርሃለሁ።

62. የመንግሥተ ሰማያት መክፈቻን ሠጥቸሃለሁና የሲኦል በሮች የማይበረቱባትን መንግሥተ ሰማያት ትዘጋና ትከፍት ዘንድ የወደድከውንም ታደርግ ዘንድ እንዲህም አለኝ "የፊት እኔ ነኝ የኋላም እኔ ነኝ የምገድልም እኔ ነኝ የምፈውስ እኔ ነኝ እኔ በአብና በመንፈስ ቅዱስ አለሁ አብና መንፈስቅዱስም በኔ ህልዋን ናቸው በሥላሴ አንድነት እኔ አለሁ።

63. ሰማይ መንበሬ ነው ምድርም የእግሬ መርገጫ ናት። ከኔ ፊት የሚቆም ማን ነው በአርአያየና በምሳሌየ አዳምን ፈጠርኩት በሱ ላይም የሕይወት እስትንፋስ እፍ አልኩበት።

64. በሱ ላይ ነባቢት ነፍስን አሳደርኩበት እቺም የማትሞት ናት በምልክትና በአምሳል አትታወቅም በመላእክት ምሳሌነትም አትታወቅም ከሰማያት መንበሩ የወደቀው ዲያብሎስንም እንዲቃወመው አደረግሁት።

65. ጴጥሮስ ሆይ እኔ ልጁ እንደሆንኩ አብ ገለጠልህ ከሱ ጋር አንድ እንደሆንኩም አስረዳህ ጴጥሮስ ሆይ እኛ መላእክትን በፈጠርናቸው ጊዜ አዳምን ፈጠርነው። በፀጋዬም ቤተክርስቲያንን ሠራኋት አፍላግንና ዕፅዋትንም በሷ ላይ

ወዕፀው። ይእቲ መንፈሳዊተ እንተትትሌዓል መልእልተኩሉ አድባር ፲ወ፰ በእመተ መንፈስ ቅዱስ።
66. ወአውሳእኩ ወእቤሎ እግዚእየ ሚመጠነ ዕመተ መንፈስቅዱስ ወይቤለኒ መጠነመዝራእት ወእራኀየ ዘሰፋሕኩ ዲበመስቀል።

67. ወመጠኑ ለዝ እምሥራቅ እስከምዕራብ ኦ ጴጥሮስ ዘተከልኩ ዕፀ መንፈሳዊተ ውስተ ገነት ወገበርኩ ውስቴታ ኩሎ ሠናያተ ከመእፈፅም በላዕሌሃ ክብርየ ወስብሐትየ ወረሰይክዋ ላተ ገነተ በአምሳለ ቤተቤተክርስቲያን እንተ በሰማያት ወአስተዳሎኩዋ ለደናግል ወለመሐይምናን ኑኃ ወግድማ ለቤተክርስቲያን መጠነ ዕባያ ለኤዶም ገነተ ትፍሥሕት ዘረሰይክዋ ማሕደረ መንፈሳውያን ደቂቀ አዳም።

68. ወፈኖክዎ ለፈያታዊ ቅድሜየ ውስተ ገነት ይዜኑ ዜና ዕርገትየ ውስተ ሰማያት ኀበአብ ኦ ጴጥሮስ እከሥት ለከ ምሥጢራትየ ዘተሥእልከኒ ወትሬኢ በዓዕይንቲከ ውስተ ሰማያት ኀበ አብ።
69. ወውእተ ጊዜ ሰገድኩ ቅድሜሁ ወእቤ እግዚእየ ወአምላኪየ አንተ ተአምር መጠነአፈቅረከ ወዘከመ

ሾምኩ ቤተክርስቲያን ከአንድ በላይ ከተራሮችም ከፍ እንድትል አደረግሁዋት ይህም በመንፈስ ቅዱስ ነው።
66. እኔም መለስኩ እንዲህም አልኩት በመንፈስቅዱስ ክንድ ስንት ያህል ነው አልኩት እሱም "መጠኑ የሚለካው እጆቼን በመስቀል ግራና ቀኝ ዘርግቼና ማሕል እጅም በመስቀል ላይ በዘረጋሁበት ነው።
67. የዚህም መጠኑ ከምሥራቅ ተነስቶ እስከ ምዕራብ ይደርሳል ጴጥሮስ ሆይ በገነት የተከልኩዋት መንፈሳዊቷ ዕፅና በሷም ላይ መልካምን ሁሉ ያደረግሁ በሷ ላይ ክብሬንና ምሥጋናየን እገልፅ ዘንድ ነው። ገነትንም አደረግሁዋት የቤተክርስቲያን ምሳሌነትም ሠጠኂት እቺም ቤትክርስቲያን በገነት ያለች ናት። እቺንም ቤተክርስቲያን ለመሐይምናንና ለደናግል እንድትሆን አዘጋጀኂት ርዝመቷና ስፋትዋ መንፈሳውያን የአዳም ልጆች በሚኖሩበት ገነት ኤዶም መጠን ነው የተሠራችው።
68. ፈያታዊ ዘየማንንም በሰማያት የዕርገቴን ዜና ከአብ ዘንድ እንዲናገር ላክሁት ጴጥሮስ ሆይ ምሥጢሮቼን እገልፅልሃለሁ። ይህንንም ለምነኸኛል ስለዚህ በሰማያት ያለውን ከአብ ዘንድ ታያለህ"።
69. በዚህ ጊዜ ከፊቱ ሰገድኩ እንዲህም አልኩ ጌታዬና አምላኬ ሆይ እነሆ የክብርህ ልዕልናና ግርማህ አውቅ ዘንድ

አአምን ብከ ናሁ አለበውከኒ ዕበየ ክብርከ ወግርማከ ወይእዜኒ አጠይቀኒ ኵሎ ዘከመተፈጥሩ ሰማያት ወመላእክት ወሥልጣናት ስነ ፆታሆሙ ወአርአያሆሙ ከመአርአያሰብእኑ ከመጽላሎት በሙኑ እንከ ኑኀ ወግድም።።

70. ወአይ ጊዜ ፈጠርኮሙ እምቅድመተፍጥርኑ ሰማያተ ወምድረ ወሚመ እምድሕሬሁ በአይወርኅ ፈጠርኮሙ ወበአይ ሰዓት።።

71. በሙኑ ኀጢአት ከመ ሰብእ ወአእምሮ ወሰሚዕ ወርእይ ወሕሊና ነስሕሳን።። -፩ኑ አርአያሆሙ አው ዘዘዚአሆሙ ራእዮሙ ወውሉጥ እንከ ራእዮሙ ወሚመ።።

72. ወዘከመ እፎ ይወፅእ እምኔሆሙ ድምፀቃሎሙ እስመ አልቦሙ ሥጋ እፎ ይከውን ነቢብ እምኀበ ዘአልቦ ልሣን ምንተይከውን እምድሕረትንሣኤ ሙታን።።

73. ወአውሥአ ወይቤለኒ "ኦ ጴጥሮስ ናሁ ተሰዓልከኒ ዕፁበ ነገረ ዘኢየአምር ሕሊና ጥበቢሆሙ ለሰብእ ወይእዜኒ ስማዕ ወለቡ ዘእነግረከ ቀዳሚ ወርኀ ዘፈጠርኩ ኔሳን ዘውእቱ ሚያዝያ።።

ያስተዋይነትህን መንገድ ገለጥክልኝ እኔ እንደማምንህና እንደማፈቅርህ አንተ ታውቃለህ አሁንም ሰማዮች፣ መላእክትና ሥልጣናት እንዴት እንደተፈጠሩ አስረዳኝ ስንት መዓርጋት አሉዋቸው አርአያቸውስ የሰው አርአያ ያለው ነውን እንደጥላ ናቸውን ጕድንና ቁመትስ አላቸውን።።

70. በየትኛውስ ጊዜ ፈጠርካቸው ሰማይንና ምድርን ከመፍጠርህ በፊት ነውስ ወይ በኋላ በየትኛው ወር ፈጠርካቸው በየትኛውስ ሰዓት በእምላካዊ ሥልጣንህ ሊፈጠሩ ቻሉ።።

71. እንደሰው ሐጢአት ሊኖራቸው ይችላልን አእምሮ መሥማት ማየትና ማሰብስ ተሠጥቶአቸዋልን ይንቀሳቀሳሉን መልካቸውስ ተመሳሳይ ነውን ወይስ ይለያያሉ ወይም ደግሞ ቁመናቸውና ምስጋናቸው ይለያያል ወይስ አንድ ነው።።

72. የቃላቸውስ ድምፅ እንዴት ሊሰማ ይችላል ሥጋ አልለበሱምና ንባባቸው እንዴት ሊታወቅ ይችላል ልሣን ከሌለው ፍጡር ንግግር እንዴት ይሰማል ከሙታን በኋላስ እነዚህ እንዴት ይሆናሉ

73. ጌታዬ ኢየሱስ ክርስቶስም መለሰና እንዲህ አለኝ "ጴጥሮስ ሆይ እነሆ አስደናቂ ጥያቄን ጠየቅሽኝ ይህን የሰዎች የጥበብ አስተሳሰብ ሊደርስበት የማይችል ነው አሁንም የምነግርህን ልብ ብለህ ስማ ፍጥረትን የጀመርኩበት ወር ኔሳን ይባላል እሱም ወርሐሚያዝያ ነው።።

74. ወቀዳሚት ዕለት ዘፈጠርኩ ዕለተእሁድ ወበቀዳሚት ሰዓት ዘዕለተ እሁድ ፈጠርክዎ ለሰማይ ወለኵሎሙ መላእክት ወዝንቱ ዘኢነገርክዎ ለሙሴ።

75. ወበዓርብ ዕለተ በቀዳሚት ሰዓት አድሐዕክዎ ለዲያብሎስ ወነሰትክዎ ለዲያብሎስ ወነሰትክዎ እመንበሩ ለቢውየ ሐሊናሁ ዘሐለየ ይረሲ ክብር ለመንግሥትየ።

76. ወአነኒ ረሰይክዎ ነኪረ እምስብሐትየ ወምኑነ እምክብርየ እስመሐለየ ትዕቢተ እኩየ ወአውሳእክዎ ወእቤሎ እግዚእየ ወአምላኪየ ወመድኅንየ ኢየሱስክርስቶስ ለምንት እንከ ፈጠርኮ ዘለሊከ አቅደሞከ አእምሮ ከመትረስዮ ሰይጣነ በዕልወቱ።

77. ወይቤለኒ ኦ ጴጥሮስ ናሁ ቀደምኩ አእምሮ ከመ ዝንቱ ዕልው ያምዕዓኒ አላ ባህቱ ፈጠርክዎ ከመይትገሠፅ በዘአነ አምፃእኩ ኵነኔ ላእሌሁ ከመኢይሄሊ ካልእ መልአክ ምክረ እኩየ ወዕልወተ ከመዲያብሎስ ለሊሁ በፈቃዱ አጥረየ ዕልወተ እኮ ባእድ ዘአገበሮ ዓሊወ።

78. ሶበ ሰኮነ እምኅቤየ ገቢረ ዕልወት ላዕሌሁ እምኢረከበ ኵነኔ ወእምኢሠዓርክዎ አላ ለሊሁ በፈቃዱ ሐለየ ለርእሱ መንበረ ክብር ወስብሐት ሊተሰ ኢተሠወረኒ ዘሀሎ ይመፅእ ላእሌሁ።

74. መፍጠርን የጀመርኩበትንም እለት እለተ እሁድ ናት ከዕለታቱ በመጀመሪያው ሰዓት ሰማይን ፈጠርኩት መላእክትንም ሁሉ ፈጠርኩ ይህንንም ለሙሴ አልነገርኩትም።

75. በዕለተዓርብ በመጀመርያው ሰዓትም ዲያብሎስን አደከምኩት ከመንበሩም ነቀልኩት እሱ መንግሥቱን ሽቷልና (ተመኝቷልና መንግሥቱንም እንደተመኘና እንደፈለገም አውቄአለሁና።

76. እኔም ከምስጋናየ እንዲለይ አደረግሁት ከክብሬም አውጥቼ እንዲናቅ አደረግሁት እሱ ትዕቢተኛ ሁኗልና ሐሳቡ ሁሉ ትዕቢትና መጥፎ ምክርም ሁኗልና እኔም መልሼ እንዲህ አልኩት "ጌታዬ መድሐኒቴና አምላኪሆይ አንተ በክሕደትቱ ሠይጣን እንደሚሆን አስቀድመህ እያወቅህ ለምን ፈጠርከው"

77. እንዲህም ብሎ መለሰልኝ ጴጥሮስ ሆይ ይህ ከሐዲ ፍጡር እኔን እንደሚያስቈጣኝ አስቀድሜ አውቅ ነበር ነገር ግን በሱ ላይ ባመጣሁት ኩነኔ ይቀጣ ዘንድና እንደሱም ሌላ መልአክ ከሐዲነትን እንዳያስብ ለማድረግ ፈጠርኩት ዲያብሎስ ማንም ሳያስገድደው በገዛራሱ ከሐዲነትን ገንዘብ አደረገ።

78. ነገር ግን እኔ በክብር ፈጠርኩት በምሕረትም ፈጠርኩት ነገር ግን ከፍ ባደረግሁት ጊዜ እሱ ሲክደኝ አወረድኩት የተለየና የራቀም ፍጡር አደረግሁት የበታችም እንዲሆን አደረግሁት በምድር ሁሉም የተጠላ ሆነ ሕዝብ ሁሉ ይጠሉታል።

79. ኦ ጴጥሮስ በከመፈጠርኩ ኩሎ በምሕረት ከማሁ ፈጠርክዎ ሎቱኒ ወኢአዘዝክዎ ይግበር እኩየ አላባሕቱ ለሊሁ ገብረ ዘከመይጼድም ልቡ ወአንሰ አልቦ ዘፈጠርኩ ወኢመነሂ ዘእንበለ እቅድም አእምሮ ዘይከውን በደሐሪ።

80. ወእሉ ዘይትኤዘዙ ሊተ ከመ ኢይ ሕድግ ዘሃለይኩ እፍጥር ዘእንበለ ሕፀት ወፈጠርኩ ኩሎ ዘሀለይኩ በፍቅር ወበአእምሮ ፈጠርክዎ ለዲያብሎስ ወአዕበይክዎ እምኵሎሙ መላእክት ወረሰይክዎ ቅሩበ ኀቤየ።

81. ወአቅደምኩ አእምሮ ከመአልቦ ዘየአሉ ትእዛዝየ እምኵሎሙ መላእክት ዘእንበሌሁ ወአልአልኩ መንበሮ ኧምኵሎሙ መላእክት ከመኢይርከብ ላእሌየ ምክንያተ ወኢይበል አዕበይከ እምኔየ ካልአነ መላእክተ እምእለ ከማየ።

82. ወበእንተዝ ዓለውኩ ትእዛዝከ ለጸመክንዮ ዕልወት ትካትስ ቅሩብ ውእቱ ኀቤየ ወይቀውም ቅድመመንበርየ ወይእሕዝ መንጦላዕተ ለቅኔ ዚአየ እንዘ ይነብብ ስብሐተ በውስተ ሠራዊተ መላእክት እለ እምታሕቴሁ ፈጠርክዎሙ።

79. ጴጥሮስ ሆይ ሁሉን በምሕረት ፈጠርኩ እሱንም ከፍጡራን ለይቼ አልፈጠርኩትም ክፉ እንዲሠራም አላዘዝኩትም። ነገር ግን እሱ ያዋጣኛል ብሎ ከሐዲነቱን ተከተለ ወደኋላ የሚደርስበትንም አስቀድሜ ሳላውቅ የፈጠርኩት ማንም የለም።

80. እነዚህ ለኔ ታዛዦች የሆኑ ያሰብኩትን እኔ እንዳልተው ምንም ሳላጓድል እፈጥር ዘንድ ወደድኩ በእውቀትና በአእምሮ በፍቅርም ያሰብኩትን ሁሉ ፈጠርኩ በዚህም ዲያብሎስን ፈጠርኩት ከመላእክት ሁሉም ከፍ አደረግሁት ከሁሉ በላይም ወደኔ ቀራቢ እንዲሆን ፈቅጄለት ከፍተኛውን ሥልጣን ይዞ ነበር።

81. እኔም ትእዛዜን የሚክድ ከመላእክት ሁሉ መካከል እንደሌለ አስቀድሜ አወቅሁ ዲያብሎስ ብቻ እንደሚክድ አስቀድሜ አወቅሁ ዲያብሎስ ብቻ እንደሚክድ አስቀድሜ አውቅ ነበር እኔ ከመላእክት ሁሉ የበላይ አድርጌ የፈጠርኩት ለክሕደቱ ምክንያት እንዳይኖረው ነው ከኔ በላይ ሌሎች መላእክትን ከፍ አደረግህ እንዳይል የሁሉ በላይ እንዲሆን አደረግሁ።

82. ይህ ባላደርግ ኑሮ ለከሐዲነቱ ምክንያት በፈጠረ ነበር። ጥንት ወደኔ ቀራቢ ነበር ከመንበሬ ፊትም ይቆም ነበር ለኔ ተገዢነቱንም ለማረጋገጥ መጋረጃን ይይዝ ነበር። ከሱ በታች አድርጌም በፈጠርኩዋቸው መላእክቶቼ መካከልም

ማሕደረ ለኵሎሙ እለ የአምኑ ብየ።

88. ኦ ጴጥሮስ ናሁ ወሀብኩከ መራኁተ ዘመንግሥተ ሰማያት ለሥርየተ ሐጢአት ወረሰይኩ ሰማያተ ወምድረ ወመላእክተ ይትኤዘዙ ለከ።

89. ኦ ጴጥሮስ እምቅድመ ሰማያት ወምድር አልቦ ዘፈጠርኩ ወኩሉ ፍጥረት ሐላፊ ወእቱ።

90. ወካዕበ አነ እቤሎ እግዚእየ ወአምላኪየ ለምንት ፈጠርኮ ለአዳም እንዘ ተአምር ከመየዓሉ ትእዛዘከ።

91. ወአውሥአ ወይቤለኒ ናሁ ቀደምኩ ፤ ኢሮተከ ዘተሥእልከኒ ይእዜኒ እከሥት ለከ ኩሎ ቀዳሚ ፈቀድኩ እፍጥሮ ለአዳም ብሩነ ወመንፈሳዌ ወባሕቱ ፈጠርኩ ውስተ ሰማይ ዘአፍቀርኩ ወለአዳምሰ ፈጠርክዎ በ፬ መዓዝኒሃ ለዓለም ወረሰይክዎ ንጉሠ ወመስፍነ ዲበምድር ከመያእምር ከመሥሉጥ ላእለኩሎሙ ፍጥረታት ወአነ ቀደምኩ አእምሮ ከመ የዓልወኒ።

92. ወባሕቱ ፈጠርክዎ በፍቅር ወበምሕረት ወአውሥአ ወይቤለኒ አእምርኬ ኦ ጴጥሮስ እምከመዘርአብእሲ ዘርኦ ውስተገራሕት የሐዝን ወሶበፈ ረየት ህየንተ፩፻ወ፳ ፩ ይትፌሣህ ዓቢየ ፍሥሐ ወይረስዕ ዘትካት ሐዘኖ ከማሁ

ለሚያምኑም ሁሉና ለኔም ማደርያ እንድትሆን አደረግሁዋት።

88. ጴጥሮስ ሆይ የመንግሥተ ሰማያትን ቁልፍ ሠጠሁህ ይህም ስለሐጢአት ሥር የት ነው። ሰማይንና ምድርንም መላእክት ሳይቀሩ ላንተ ይታዘዙ ዘንድ አደረግሁ።

89. ጴጥሮስ ሆይ ሰማይና ምድር ከመፈጠራቸው በፊት የፈጠርኩት የለም ፍጥረት ሁሉ ሐላፊ ነው።

90. እኔም በድጋሚ ጌታየና አምላኬ ሆይ እንደሚበድል እያወቅህ አዳምን ለምን ፈጠርከው" በማለት ጠየቅሁት።

91. ጌታዬና አምላኬ መለሰልኝ እንዲህም አለኝ "የጠየቅኸኝን አስቀድሜ መልሼልሀለሁ አዳምን መንፈሳዊና ብሩህ አድርጌ እፈጥረው ዘንድ ወደድኩ በሰማይ ውስጥም የወደድኩትን ሁሉ ፈጠርኩ አዳምን ግን በዓራቱ መዓዝነ ዓለም የበላይ አድርጌ ፈጠርኩት ንጉሥነትንና መስፍንነትንም ሠጠሁት በምድር ላይ ከሁሉ በላይ አደረግሁት በዚች ምድር ባሉት ፍጡራን በሙሉ የበላይነትን ሠጠሁት ነገር ግን እንደሚክደኝ አውቅ ነበር።

92. ነገር ግን አዳምን በፍቅርና በምሕረት ፈጠርኩት አለኝ እንዲህም አለኝ ጴጥሮስ ሆይ ልታውቀው የሚገባህ ጉዳይ አለ ገበሬ ዘር ሲዘራ ዘሩን በማጣቱ ለጊዜው ያዝናል ባንድ ምትክ ሰላሳና ስድሳ መቶም ባፈራለት ጊዜ ግን ይደሰታል

አነኒ ፈጠርክዎ ለአዳም ወመሀክዎ እሞት ወሶበ ዓለወኒ አምፃእኩ ላእሌሁ ሞተ ወኢተከዝኩ በእንቲአሁ።

93. ኦ ጴጥሮስ አነ ፈጠርክዎ ለአዳም ሕያወ ወአዘዝክዎ ይዕቀብ ትእዛዛትየ ወይርሐቅ እምዕልወት ወአለበውክዎ ኵሎ ወእቤሎ አባሕኩከ ትግበር ወነገርኩከ ሠናየ ወእኩየ ኢትሕስስ ትዕቢተ ከመዲያብሎስ ዘአዕበየ ርእሶ ወወድቀ እምክብሩ ወኢትብላዕ እምዕፀ እንተትፈሪ ሞተ።

94. እመሰ በላዕከ ሞተ ትመውት ለእመኢሰማዕከኒ ቃልየ ወኢዐቀብከ ትእዛዝየ አወፅአከ እምገነት ወአነብረከ ውስተምድር ርግምት እንተታወፅእ ሦከ ወአሜከላ ወእመሰ ኢበላዕከ ወኢለውከ ትእዛዝየ ዘአዘዝኩከ ኢትብላዕ እምኔሁ ኢይቀትልከ አላ ትነብር ሕያወ ለዓለም።

95. ኦ ጴጥሮስ ናሁ አእመርኩ ከመዲያብሎስ ያስሕቶ ለዓለም ወለአዳም ያመፅእ ዕልወተ ወበእንተዝ እቤሎ ዕቀብ ትእዛዝየ ወረሐቅ እምዕልወት ወኢትብላዕ እምዕፀ ወአእሚርየ ከመየዓልወኒ ትእዛዝየ ፈጠርክዎ ሕያወ

የቀድሞውንም ሐዘኑ ይረሳል እንደዚሁ ሁሉ እኔም አዳምን ፈጠርኩት ራራሁለትም ከሞትም አዳንኩት ትእዛዜን ባፈረሰ ጊዜ ግን በሱ ላይ ሞትን አመጣሁ አላዘንኩም (እሱን በመፍጠሬ)።

93. ጴጥሮስ ሆይ እኔ አዳምን ሕያው አድርጌ ፈጠርኩት ትእዛዜንም ይጠብቅ ዘንድና ከጥፋትም ይርቅ ዘንድ አዘዝኩት ልትሠራው የሚገባህን ትሠራ ዘንድ መብት ሠጠሁህ ክፉውንና ደጉንም ለይቼ አስረዳሁህ ትዕቢትን እንደዲያብሎስ እንዳትፈልግ አልኩት ዲያብሎስ በትዕቢት ራሱን ከፍ ስላደረገ ከመንበሩ ወደቀ አንተም ሞትን ከምታፈራ ዕፀ እንዳትበላ አልኩት።

94. ከእፅዋ ከበላህ ሞትን ትሞታለህ ቃሌን ካልሰማህና ትእዛዜን ካልጠበቅህ ከገነት አስወጣሃለሁ በተረገመችውም ምድር እንድትኖር አደርጋሃለሁ። ምድር ስለተረገመች አሾህንና አሜከላን ታበቅላለች ከተከለከለችው እፅ ካልበላህና ትእዛዜን ከጠበቅህ ሞትን አትሞትም ነገር ግን እስከዘላለሙ ሕያውና ደስተኛ እንደሆንክ ትኖራለህ" አልኩት።

95. ጴጥሮስ ሆይ ዲያብሎስ ዓለምንና አዳምን እደሚያስታቸው አውቅ ነበር ይልቁንም በአዳም ላይ የኔን ትእዛዝ አፍራሺነት እንደሚያመጣበት አውቅ ነበር። ስለዚህም ትእዛዜን ጠብቅ ከተከለከለውም ዕፅ አትብላ አልኩት ትእዛዜንም

ወመዋቴ ወረሰይክዎ ዘፈጠርክዎ እምኔሁ ቱሱሐ በእሳት ወነፋስ ወማይ።

## ምዕራፍ ፯ ተሳእሎ ጴጥሮስ በእንተ ነገደ መላእክት ወበእንተ ገነት ወበእንተ ካልኣን

1. ኦ ጴጥሮስ ናሁ ነገርኩከ ትስብእትየ ከመበእንተ ትስብእትየ ፈጠርክዎ ለአዳም ወበሥጋ ዘአውፃእክዎ ለአዳም እምገነት ቦቱ ዳግመ አገብኦ ውስተ ገነት ኦ ጴጥሮስ ብየ ምሥጢር ሕቡእ ዘኢየትአውቅ ወአንስ ኢይፈቅድ እክሥት ለሰብእ ወሰሚዕየ ዘንተ ቃለ እምኀበ እግዚእየ ወአምላኪየ ሰገድኩ ቅድሜሁ ሰዓልኩ ወአንቃዕዶኩ ኀቤሁ ወእቤሎ ንግረኒ እግዚእየ ዘከመ እፎ ውእቱ ዘመደ መላእክት።

2. ወአውሥአ ወይቤለኒ ዘመደ መላእክትሰ ብዙኀን እሙንቱ ወኢኮነ ፩ ራእዮሙ እስመቦ እምኔሆሙ ዘ፬ ገፁ ወቦ እምኔሆሙ ዘኩለንታሁ ገፅ ወቦ እምኔሆሙ ዘብዙሕ ዓዕይንቲሁ ወቦ ዘኩለንታሁ ዓዕይንት ወቦ ዘኩለንታሁ ፀዳል ዘይፈደፍድ እምብርሃነፀሐይ።

3. ወቦ እምኔሆሙ ዘ፬ ገፁ ዘይመስል ከመገፀሰብእ ወቦ እምኔሆሙ ዘ፬ቱ ክነፊሁ ወለለ፩ እምእሉ መላእክት ቦሙ

እንደሚያፈርስ አስቀድሜ ስላወቅሁ መዋችና ሕያው አድርጌ ፈጠርኩት እሳት ውሃና ነፋስ ከተቀላቀሉበት አፈርም ፈጠርኩት።

## ምዕራፍ ሰባት የጴጥሮስ ስለመላእክት ነገድ ስለገነትና ስለሌሎችም ምሥጢራት ከጌታችን መረዳት

1. ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ለጴጥሮስ ጴጥሮስ ሆይ የትስብእቱን ምሥጢር ነገርኩህ ሰው ስለመሆኔንም አዳምን እንደፈጠርኩትና ከገነት ለብሶት የወጣውን ሥጋ ለብሶ ወደገነት እንደሚመለስም ገለፅኩልህ ጴጥሮስ ሆይ ለሰው ልገልፀው የማልፈልገው ምሥጢርም አለኝ። እኔም ከጌታዬና አምላኬ ይህን ሰምቼ ከፊቱ ሰገድኩ ለመንኩም ወደሱም አንጋጠጥኩ እንዲህም አልኩ። "ጌታየ ሆይ የመላእክት ነገዳቸው እንዴት ነው?"

2. እሱም መለሰ እንዲህም አለኝ የመላእክት ወገኖች ብዙ ናቸው አርአያቸውም አንድ አይደለም አራት ገፅ ያለው መልአክ አለ ሁለመናው (መላአካላቱ) ገፅ የሆነ አለ ብዙ ዓይኖች ያሉትም አለ ሁለንትናው ዓይን የሆነም አለ ሁለንትናው ከፀሐይ ብርሃን የበለጠ ብርሃን ያለውም አለ።

3. ከነሱ መካከል የሰው ፊት ያለውና አራት ፊት ያለው አለ። ከነሱ መካከል አራት ክንፍ ያለው አለ። ከነዚህ መላእክት

ስም ወከመዝ አስማቲሆሙ ለመላእክት ወሊቃነ መላእክት አጋእዝት ወሥልጣናት ኃይላት ወመናብርት አርባብ ኪሩቤል እለብዙሐት አዕይንቲሆሙ ወሱራፌል እለ፮ክነፊሆሙ።

4. ፱ቱ ነገደ መላእክት ወእም፩ ነገደ መላእክት እስከ ካልእ መዓርግ ዘመላእክት ከመ ማእከለ ሰማይ ወምድር ወአዲ ማእከሎሙ ፀዳል ወብርሃን ወብሩሕ ፈድፋደ ከመ ይትናገሩ በበይናቲሆሙ ወያስተዐፅቡ ፍጥረቶሙ ወየአኩቱ ስምየ ልዑለ እስመ ረከብኩ ውስተአፉሆሙ ነቢበ ዕበየ ግርማ።

5. በ እምኔሆሙ ዘይዜምር ወበ እምኔሆሙ ዘይቄድስ ወበ እምኔሆሙ ዘይዌድስ ወበ እምኔሆሙ ዘየአኩት ወበእምኔሆሙ ዘይሴብሕ ወበ ዘይባርክ ወበ ዘይየብብ ወከመዝ ሕይወቶሙ እስከ ለዓለመ ዓለም።

6. ኦ ጴጥሮስ እስመኢፈጠርክምሙ ለእሉ ለጻሕቅየ ኀቤየ ዘእንበለ ዳእሙ ፈቀድኩ እፀግምሙ ብዕልየ ወክብርየ እስመ እምቅድመ እፍጥር ኩሎ ፍጥረተ ስብሐትየ ምስሌየ ውእቱ።

7. ወሶበ ፈጠርክዎሙ ለመላእክት ረሰይክዎሙ በዘዚአሁ ጥዑመ ዜማ ወማሕሌት እሉ መላእክት መንፈሳውያን እሙንቱ ወአልበሙ ሥጋ ወሶበ ይወርዱ መላእክት

ለያንዳንዳቸው ስም አላቸው የመላእክትና የሊቃነመላእክት የአጋእዝትና የሥልጣናት የኃይላት እንዲሁም የመናብርት አርባብ ኪሩቤል ናቸው ኪሩቤል ብዙ ዓይኖች ያሉዋቸው ናቸው ሱራፌልም ስድስት ክንፍ ያላቸው ናቸው።

4. ዘጠኝ ነገደመላእክት አሉ ካንዱ የመላእክት ነገድ ወደሌላው የመላእክት ነገድ ድረስ ያለው ርቀት የሰማይና የምድር ርቀት ያህል ነው። በመካከላቸውም ፀዳልና ብርሃን አለ። የዚህም ብርሐን እጅግ የደመቀ ነው። ይህም እርስበርሳቸው ይናገሩ ዘንድ ነው ስለራሳቸውም አፈጣጠር እጅግ ያደንቁ ነበር። ስሜንም ያመሰግናሉ ከነሱ አፍ መልካም ምስጋናን አገኘሁ።

5. ከነሱ ውስጥ የሚዘምር አለ የሚያወድስ አለ የሚቀድስ አለ ከመካከላቸው የሚያስታኩት አለ። ከነሱ መካከልም የሚያመሰግን አለ የሚባርክ አለ እልል የሚል አለ። የነሱ ሕይወት እስከዘለዓለሙ በዚህ የተመሠረተ ነው።

6. ጴጥሮስ ሆይ እንዲያገለግሉኝ እነዚህን አልፈጠርኩዋቸውም ነገር ግን የኔን ብዕል አድላቸው ዘንድና ክብሬንም አጕናፅፋቸው ዘንድ ብቻ ፈጠርኩዋቸው እኔ ፍጥረታትን ሁሉ ከመፍጠሬ አስቀድሞ ምሥጋናየ ከኔ ዘንድ ነበረ።

7. መላእክትን በፈጠርኩዋቸው ጊዜ ያመሰግኑኝ ዘንድ አደረግሁዋቸው። በጥዑም ዜማና በተለያየ ማሕሌት ያመሰግኑኛል። እነዚህ መላእክት መንፈሳውያን ናቸው ሥጋ

ዲበምድር አልበሙ ድምፅ ወኢይሰማዕ ድምፀ ክነፊሆሙ።

8. ወአልቦ አሠር ለምክያደተ እገሪሆሙ ወይቀልል ሩፃቶሙ እምነፋሳት ወይትፌነው ለምሥጢራት መልእክትየ ወየዓቅብዎሙ ለእለ ይጠመቁ በስመአብ ወወልድ ወመንፈስቅዱስ ወለኵሎሙ እለየአምኑ ብየ እፌኑ ለለ፩፩ ፪ተ መላእክተ ፩ በየማኑ ወ፩ በፀጋሙ ወየዓቅብዎሙ እምኵሉ እኩይ ወእለሰ ኢየአምኑ ብየ አርሕቆሙ እምሣህልየ ወሞሕረትየ።

9. ወሶበ ሰማዕኩ ዘንተ ነገረ በሀቤሁ ሰገድኩ ቅድሜሁ ወእቤሉ እግዚእየ ወአምላኪየ ወልድ ዋሕድ ዘመጻዕከ ውስተ ዓለም ለመድኅኒተ ሰብእ ንግሮ ለገብርከ ዜናሃ ለገነት ውስተ ምድርኑ ይእቲ ወሚመ ውስተ ሰማይ።

10. ምንት ውእቱ ዕፅ ዘያሌቡ ሠናየ ወእኩየ ዘአዘዝከ ለአዳም ከመ ኢይብላዕ እምኔሁ ወምንት ውእቱ ዕፀሕይወት ወእፎ ተከድኑ አዳም ወሔዋን ቈፅለ በለስ በውስተ ገነት ይውእኑ እንከ ፀሐይ ወወርሕ ውስተ ገነት ወቦኑ እንከ መዓልት ወሌሊት።

አልለበሱም ወደምድር ሲወርዱ ድምፅ የላቸውም የክንፉቸውም እንቅስቃሴ አይሰማም።

8. ለእግራቸው ኮቴም ምልክት የለውም ሩጫቸው ከነፋሳት ይቀላል። ምሥጢራቴን ለመፈፀም ይላካሉ በአብ በወልድ በመንፈስ ቅዱስ ስም የሚጠመቁትን ይጠብቋቸዋል በኔ አምነው በስሜ ለተጠመቁት ሁሉ በነዚህ መላእክት ጥበቃ ይደረግላቸዋል ለያንዳንዱ ክርስቲያን ሁለት ጠባቂዎች መላእክት ይላኩለታል በግራና በቀኝ በመሆንም ይጠብቁታል ከክፉ ነገር ሁሉ እንዲታቀብ ያደርጉታል ላላመኑብኝ ግን ከይቅርታየና ከምሕረቴ አርቃቸዋለሁ።

9. ይህን ከሰማሁ በኋላ ከፊቱ ወድቄ ሰገድኩ ጌታዬና አምላኬ ሆይ የገነትን ሁኔታ ንገረኝ ገነት በሰማይ ላይ ነው የምትገኘው ወይስ በምድር ላይ አንተ የሰውን ልጆች ታድን ዘንድ ወደዚህ ዓለም መምጣትህን አውቃለሁ ይህን ምሥጢር ግለፅልኝ" በማለትም ጠየቅሁት።

10. አስተዋይ ልቡና እንዲኖር የሚያደርግ ክፉውንና ደጉን የሚያሳውቅ ዕፅ ምን ዓይነት ዕፅ ነው። ከዚህ ዕፅ አዳም እንዳይበላ ተከልክሏል ዕፀ ሕይወት ማለት ትርጉሙ ምንድር ነው አዳምና ሄዋንስ የበለስ ቅጠል እንዴት ለበሱ በገነት እያሉ የበለስን ቅጠል ሊለብሱ የቻሉት ፀሐይና ጨረቃ ከዚያ አሉን ሌትና ቀንስ ይፈራረቃሉን።

11. አው መብልዕ ወመስቴ ወዕፀውኒ ዘውስቴታ ከመ ዕፀወዝንቱ ዓለም ወቦኑ እንጋ ቁር ወዋዕይ ወቦኑ ረሐብ ወፅምዕ ወእለ ይነብሩ ውስቴታ ይትፌቀድኑ ልብስ ወአራዝ ወሚመ አልቦ ወቦኑ ህየ ሕንፃ ዕነዕ ወእምአይቴ ይወፅኡ ፬ አፍላግ ወይሰቅዩዋ ለምድር።

12. መኑ የዓቢ መንግሥተ ሰማይኑ ወሚመ ገነት ወሚ መጠነ ኑኃ ወግድማ ኃላፊትኑ ከመ ዝንቱ ዓለም ወሚመ ትነብር ለዓለመ ዓለም ወለዝሉፉ።

13. ወአውስአ ወልደ እግዚአብሔር ወይቤለኒ ኦ ጴጥሮስ እፎ ፅሕቀ አንተ ለተሐስሶ ምሥጢራትየ ለገነትሰ አንበርናሃ ውስተ ኤዶም እምድሕረ ፈጠርነ ሰማየ ወምድረ ኀበኢይረክባ ጽልመት አላ ትነብር ብርሕተ ወንፅሕተ ግርምተ ወልዕልተ። ይእቲ እምዛቲ ምድር መጠነ ምሥራቅ እስከ ምዕራብ።

14. ወቦ ውስቴታ ሠለስቱ ኃዋሕው ወቀዳሚት ኖኅት ረሰይኩ መልእልተ ጕልጎታ ኀበ ተቀብረ ሥጋየ ዘነሣእኩ እምአዳም ወለዳግማዊትሰ ኖኅት ረሰይክዋ መልእልተ ደብረ ዘይት ወአንተሰ ኦ ጴጥሮስ ትነብር ታሕቴሃ

11. በገነት መብልና መጠጥ አለን ብዙ ዛፎችስ ከዚያ ይገኛሉን ዛፎቹስ የዚችን ምድር ዛፍ ይመስላሉን ሙቀትና ቅዝቃዜ በገነት ይኖራልን ረሐብና ጥምስ አለን። ከዚያ ለሚኖሩ ልብስ ያስፈልጋልን ወይስ ይህ ሁሉ የለም ይሆን ለሰዎች መኖርያ ሠው ሠራሽ ግንብ ከዚያ ይኖራልን እነዚያ ምድርን የሚያጠጡ አራት ወንዞችስ ከየት ይመነጫሉ።

12. ከገነትና ከመንግሥተ ሰማይ ማን ይበልጣል የገነት ቁመትና ርዝመትስ ምን ያክል ነው ገነት ይህ ዓለም ሲያልፍ ታልፋለችን ወይስ ሳታልፍ አሁን ባለችበት ለዘለዓለም ፀንታ ትኖራለች? አልኩት።

13. ወልደ እግዚአብሔር ክርስቶስ የሚከተለውን "ጴጥሮስ ሆይ የኔን ምሥጢራት ለማወቅ እጅግ ተግተሃል ገነትን በኤዶም ውስጥ አኖርናት ይህንንም ያደረግነው ሰማይንና ምድርን ከፈጠርን በኋላ ነው ገነትን ጨለማ እንዳያገኛት በማድረግ ነው የፈጠርናት። ገነት ብሩህ ሁና በንፅሕና በመዓርግ በግርማ ያለች ናት ከፍ ያለችም ናት እሷ ከዚች ምድር ከፍ ትላለች። እሷም ከምሥራቅ እስከ ምዕራብ በምድር መጠን ትደርሳለች።

14. ሶስት መስኮቶች በገነት አሉ አንደኛው መስኮት ከአዳም የለበስኩት ሥጋ በተቀበረበት ጎልጎታ አቅጣጫ አንፃር ይገኛል ሁለተኛው መስኮት ደብረዘይት በሚገኝበት ሥፍራ ትይዩ ይገኛል። ይህ ቦታ አንተ ያለህበት ነው ሦስተኛው መስኮት

ወሣልስ ኖኅት መልእልተ ደብረሲና፡፡

15\. ገነትሰ ታሕተ መንበርነ መንግለ ምሥራቅ ወፀዳሉ ይፈደፍድ እምብርሃነ ፀሐይ ወይወፅእ እምውስቴታ ዔና መዓዛ ሠናይ ዘአልቦ ዘከማሁ ውስተ ኵሉ ምድር ወአዲ ይእቲ ማሕደረ መለኮት፡፡

16\. መላእክትሰ ብሂል ዕፀዋት እለትኩላን ውስቴታ ወ፬አፍላግ እለይሣቅዩ ዓለመ ይፈለፍሉ እማይ ዘእምታሕተ መንበረ ስብሐትየ ናሁ ረሰይኩ ፬ቱ ሙሓዛት እለ የኃልፉ እምባሕረ ነፋሳት ወይወርዱ ፍጡነ ውስተ ኤዶም ወእምህየ ይውሕዝ ማይ ወይሰቅያ ለዓለም፡፡

17\. ወእለ ይነብሩ ህየ ይፈቅዱ በሊዓ ወሰትየ ወአልቦ ውስቴታ ቁር ወዋዕይ ወእምጣዕመ ዔና ዘውስተ ገነት የዓትት ፍቅረ በሊዕ ወሰትይ፡፡

18\. ወዕፀዊሃሰ ለገነት ብሩሃን ወቅዱሳን መላእክት እሙንቱ እለኢኮኑ እምዕፀወ ዝንቱ ዓለም ሐላፊ ወኢያፀርዑ ስብሐ ወዘምሮ ወዕፅ ዘሀሉ ውስተ ገነት ዘያሌቡ እኩየ ወሰናየ ለልየ አእምር ውእተ ዕፀ፡፡

19\. ኦ ጴጥሮስ ኃሠሠ አቡከ አዳም ከመ ዲያብሎስ ዘፈቀደ ይኩን አምላከ ወይንሣእ ሥልጣነ ላእለ ዘሴምክዎ ላእሌሆሙ እስመ በእንተዝ በልዐ እምውእቱ ዕፀ ዘአዘዝክዎ ኢይብላዕ እምኔሁ ወሶቤሃ አእመረ ፍትወተ፡፡

በደብረሲና ትይዩ ይገኛል፡፡

15\. ገነት በመንበራችን ከወደታች ሁና በምሥራቅ በኩል ትገኛለች ብርሃንዋም ከፀሐይ ብርሃን ይበልጣል ከሷም መልካም መዓዛ ያለው ሽታ ይወጣል የዚህ መዓዛ ተመሳሳይ በምድር ፈፅሞ አይገኝም የመለኮት ማደርያም ናት፡፡

16\. የገነት ዛፎች በመላእክት ይመሰላሉ ዓለምን የሚያጠጡ አራቱ ወንዞች ከምሥጋናየ መንበር ሥር የማሚመነጩ ናቸው፡፡ እነሆ አራት የውሃ መውረጃዎችን አዘጋጀሁ እነዚህ የውሃ መውረጃዎች የነፋሳትን ባሕር የሚያልፉ ሁነው ወደኤዶም ይወርዳሉ፡፡ ከዚሁም ውሃ ይመነጭና ዓለምን ያጠጣታል፡፡

17\. በገነት የሚኖሩ መብላትና መጠጣት ይፈልጋሉ በገነት ብርድና የፀሐይ ቃጠሎ የለም ከገነት የሚመነጨው መልካሙ ሽታ የመብላትንና የመጠጣትን ፍላጎት ያስወግዳል፡፡

18\. የገነት ዛፎችስ እንደዚህ ዓለም ያሉ ዛፎች አይደሉም ብሩሃን መላእክት ናቸው፡፡ እነዚህም መላእክት እኔን ማመስገንና መዘመርን አያቋርጡም በገነት ስላለውና መልካምንና ክፉውን የሚያሳውቀውስ የሱን ምንነት የማውቅ እኔ ብቻ ነኝ፡፡

19\. ጴጥሮስ ሆይ ዲያብሎስ አለቅነትን ሠጥቼ በብዙ መላእክት ላይ ስለሾምኩት አምላክ ሁኖ በነሱ ላይ እንዲመለክ እንደፈለገ አባትህ አዳምም እንዳይበላ ከከለከልኩት ዕፀ የበላው አምላክነትን ስለፈለገ ነው ወድያውም የፍትወት ተገዢ ሆነ

20. ውእቱ ዕፅ ፈረየ ሞተ ዘ፪ ፍናዊሁ አ፩ እስመ ፈቀደ ይኩን አምላከ ዘኢይትከሀል ይኩን ወዳግመ ዘአዘዝክዎ ዓለወ ትእዛዝየ እስመ በጊዜ አዘዝክዎ ኢኮነ ዐብደ ባህቱ ለአብድስ ዘኢለበወ ዐቂበ ትእዛዝ ኢይደልዎ ኩነኔ።

21. አላ ውእቱ ለባዊ ወጠቢብ ወኧምብዝሐ ጥበቢሁ ሰመየ ስሞሙ ለኩሎሙ ፍጡራን በበአስማቲሆሙ።

22. ኦ ጴጥሮስ ዕፀው እለ ውስተ ገነት መላእክት እሙንቱ ወንሕነ ውእቱ ዕፅ ዘውስተገነት ዘያሌቡ ሠናየ ወእኩየ ኦ ጴጥሮስ አነ ውእቱ ዕፀሕይወት ወምሕረት ወዘበልዓ እምኔሁ ሕይወተ ዘለዓለም የሐዩ አቡየ ዕፀ ርትዕ ወጽድቅ ወአነኒ ሣሕል ወምሕረት ወነፍስ ዕፀ ሕይወት ውእቱ።

23. ኦ ጴጥሮስ ኢይበውእ ውስተ ገነት ጽልመት ወኢፀዳል እስመኩለንታሃ ብርሃን ዘይፈደፍድ አምብርሃነ ፀሐይ ወአልቦ ዘይትማሰሎ ለዔና መዓዛ ወአልቦ ህየ ሞት ወለእለ ይነብሩ ውስቴታ አልቦሙ ደዌ ወሕማም።

(ፍትወትን አወቀ)።

20. ይህ ዕፅ ግን ሞትን አፈራ ይህም ሞት ሁለት መንገድ አለው አንደኛው ሲሆን የማይችለውንና የማይገባውን አምላክነትን መመኘቱ ሁለተኛው እኔ ሳዘው ጤናማ አስተዋይ ሰው ነበረ ትእዛዜን ሲያፈርስ ግን ዓበደ በዕብደቱ ሥሕተት ላይ ለወደቀ ኩነኔ አይገባውም አዳም ግን ጤናማ ኑሮ ትእዛዜን በማፍረሱ ዓበደ።

21. አዳም እብድ ሁኖ አልተፈጠረም አስተዋይ ብልሐተኛ ሁኖ ነው የተፈጠረው ከጥበቡ ብዛት የተነሳም ፍጡራንን ሁሉ በየስማቸው ሰየሞአቸው።

22. ጴጥሮስ ሆይ በገነት ውስጥ ያሉ ዛፎች መላእክት ናቸው በሌላ በኩል የገነት ዛፎች እኛ ነኝ መልካሙንና ክፋውን የሚያሳውቀው የገነት ዛፍ ማለት እኛ ነን ጴጥሮስ ሆይ የሕይወት ዛፍ ማለት እኔ ነኝ የምሕረትም ዛፍ ነኝ ከኔ የበላ የዘልዓለም ሕይወት አለው አባቴ የርትእ ዛፍ ነው የዕቅድም ዛፍ ነው እኔ ደግሞ ይቅርታና ምሕረት ነኝ መንፈስ ቅዱስም የሕወት ዛፍ ነው።

23. ጴጥሮስ ሆይ ጨለማ ወደገነት አይገባም ገነት ሁለንትንዋ ብረሃን ናት ይህም ብርሃን ከፀሐይ ብርሃን ይበልጣል የሚመሳሰለውም የለም በገነት ለሚገኘው መዓዛም የሚስተካከለው የለም ሞት በገነት የለም በገነት ለሚኖሩ

24. ኢይበውእ ህየ ርኩሰት ወዕልወት ርኩሳን ወዕልዋን (ኢይበውእዋ) ወኢይፀራዕ እምውስቴታ ስብሐት መዓልተ ወሌሊተ ከመኢየሩሳሌም እንተ በሰማያት ወይፈደፍድ ብርሃና እምነ ፀሐይ ዘኢይክል ልሣነ ሰብእ ዜንዎቶ እስመ ፅንዓ ኀይልየ ወብረሃንየ ወግርማየ የሕድር ላዕሌየ

25. ኦ ጴጥሮስ ሃደግክዋ ለገነት ወአንበርክዋ ታሕተ መንበረ መንግሥትየ ኦ ጴጥሮስ ዛቲ ገነት ድሉት ይእቲ ለኄሩያንየ እለ አሠመሩኒ በሕይወቶሙ ኦጴጥሮስ አልቦ ውስተ ገነት ክረምት ወኢሐጋይ ወአልቦ ወስቴታ ፍትወተ ዝንቱ ዓለም ኢበሊዕ ወኢስትይ እስመ ዜና መዓዛሃ ያፀግብ ነፍሳተ።

26. ወለእለ ይነብሩ ውስቴታ አልቦሙ ሕሊና ትካዘ ዝንቱ ዓለም ኢይርህቡ ወኢይፀምኡ ወኢይፈቅዱ ትዕይርተ ወትዝሕርተ ወኢየዓርቁ

27. ቈፅለ በለስ ዘተሰምየ ወከመ ይልበሱ አዳም ወሄዋን አኮ ቈፅለ በለስ አላ ፀጋ ውእቱ ኦ ጴጥሮስ ኩሉ ግብራ ለገነት መንክር ወመድምም

ሕመም ደዌ ሞት የለባቸውም።

24. ወደገነት ህግአፍራሽነት ተላላፊነትና ርኩሰት አይገባም ህግ ተላላፊዎችና ርኩሳት ወደገነት አይገቡም በገነት ሌትና ቀን ምሥጋና አይታጐልም ይህም እኳኋን እንደ ሰማያዊቷ ኢየሩሳሌም ያለ ነው የገነት ብርሃን ከፀሐይ ብርሃን ይበልጣል የዚህ ብርሃን መጠን በሰው አንደበት ሲገለፅ አይችልም የራሴ ግርማ ፅናት ኃይሌና ብርሃኔ በኔ ላይ ያለ ነውና።

25. ጴጥሮስ ሆይ ገነትን አከበርኩዋት በመንግሥቴ በታችም አስቀመጥኩዋት ጴጥሮስ ሆይ እቺ ገነት ለደጋግ ሰዎች ብቻ የተዘጋጀች ናት ደጋግ ሰዎች ማለትም በሕይወት ዘመናቸው ፈቃዴን የፈፀሙ ናቸው። ጴጥሮስ ሆይ በገነት ክረምት የለም በጋም የለም የዚህ ዓለም ፍትወት የለም መብል መጠጥ የለም በዚችው በተመረጠችውና በተቀደሰችው ገነት የሚኖሩ ሁሉ በሷ በሚፈልቀው መልካም መዓዛ ይኖራሉ።

26. በዚችው ገነት ውስጥ ለሚኖሩ ሁሉ የዚህ ዓለም ጣጣ ውጣውረድ የለባቸውም አይራቡም አይጠሙም መገዳደርም ሆነ መታበይ በነሱ ዘንድ ፈፅሞ አይታወቅም የለምም በፀጋ የተዋቡ ስለሆኑም አይራቆቱም።

27. የበለስ ቅጠልን አዳምና ሄዋን እንደለበሱ የሚባለው እነሱ ለብሰውት አይደለም ፀጋ ሲለያቸው ሐፍረታቸውን በእጃቸው ነው የሸፈኑት ጴጥሮስ ሆይ የገነት አሠራር እጅግ አስደናቂና

28. መንግሥተ ሰማያት የዓቢ. ወትከብር ወትትሌዓል እምኔሃ ወኵሉ ዘድልው ለወንግሥተ ሰማያት ይቀድም በዊዓ ውስተ ገነት ወይትፌሣሕ በውስቴታ ወይትመየጥ ውስተ መንግሥተ ሰማያት ኀበ ኢይበሊ. ወኢየማስን

29. ኦ ጴጥሮስ ብየ ብዙሕ ዓንቀጽ ወማሕደር ግሩማን ዘየሐድር ብርሃንየ ውስቴቶን ዘአስተዳሎኩ ለነፍሰጻድቃን ወኄራን።

30. ኦ ጴጥሮስ ናሁ ወሀብኩከ መራኁተ መንግሥተ ሰማያት ወምድር ወረሰይኩ ኩሎ ውስተ እዴከ ወዝንቱ ክብር ዘእቤለከ ለከ ውእቱ ማሕደረ ብረሃን ዘሀሎ ውስተሰማያት። ድሉት ይእቲ ለእለ የአምኑ ብየ።

31. ወዘንተ ብሂሎ አርመመ ወእምዝ ሰገድኩ ቅድሜሁ ወእቤሎ ተሰሀሎ እግዚኦ ለገብርከ ወአብፅሖ ይንብብ ቅድሜከ ወአውሥአ ወይቤለኒ ኦ ጴጥሮስ ንግር ዘተፈቅድ ወሰዓል ዘትፈቱ ወአንሰ ኢይከልእ ሥእለተከ ወካዕበ እቤሎ ኦ እግዚኦ ንግሮ ለገብርከ ማሕደሮሙ ለጻድቃን ወለነቢያት እለ የአምኑ ብከ ወዘከመእፎ ይነብሩ መኀይምናን እምቅድመ ዳግም ምፅአትከ።

የሚያስገርም ነው።

28. መንግሥተ ሰማያት ግን ከገነት ከፍ ትላለች ትበልጣለች ትከብራለችም መንግሥተ ሰማያትን ለመግባት የታደለው አስቀድሞ ወደገነት ይገባና በዚሁ ይደሰታል ከዚያ በዚህ ቀን ያልፋል ወደማይባለው መንግሥተሰማያት ይገባል።

29. ጴጥሮስ ሆይ ለጻድቃንና ለደጋግ ሰዎች ያዘጋጀኋቸው ግሩማን የሆኑ በውስጣቸው ብርሃን ያለባቸው ብዙ በሮችና ማደርያዎች አሉ።

30. ጴጥሮስ ሆይ የመንግሥተሰማያትንና የምድርን ቁልፍ ሠጠሁህ ሁሉንም በእጅህ አስረክቤሀለሁ ይህንንም የምገልፅልህ ክብር አንተን የሚመለከት ነው። የብርሃን ማደርያ የተባለው የክብር ቦታ ላንተ ይሠጣል ይህም በሰማያት ያለ ሲሆን ካንተ ሌላ እኔን የሚያምኑ ሁሉ እንዲገቡበት አስቀድሞ የተዘጋጀ ነው" አለኝ።

31. ይህን ሁሉ ተናግሮ (ጌታችን መድሐኒታችንና አምላካችን ኢየሱስክርስቶስ) ዝም አለ። ከዚያ እኔ ከፊቱ ሰገድኩ አቤቱ ሆይ አገልጋይህን ይቅር በለው ከፊትህ ይናገር ዘንድም ፍቀድለት ብየ ለመንኩት። እሱም መለሰ እንዲህም አለኝ "የምትፈልገውን ተናገር የምትወደውንም ለምን እኔ ልመናህን አልከለክልም" እኔም ስመልስለት እንዲህ አልኩት " አቤቱ ጌታዬ ሆይ የጻድቃንንና የነቢያትን ማደርያ (መኖርያ) የት

32. ወይቤለኒ እግዚእየ ወአምላኪየ "ኦ ጴጥሮስ እትወከፍ ሥእለተከ ወእነግረከ ማኅደሮሙ ለመሐይምናን እለ የአምኑ ብየ ለጻድቃን ወለነቢያት ወለባእዳንሂ እምድሕረ ዕርገትየ እምድር ውስተ ግሩም ማሕደርየ ወማሕደሮሙ ለጻድቃን ወለንፁሐን እለተጠምቁ በስምየ ወአምኑ ብየ ወነሥሑ እምቅድመ ይሙቱ።

33. ገነት ይእቲ እንተ ተከልክዋ ውስተ ኤዶም ህየ ማሕደሮሙ ወየዓርፉ ውስቴታ እስከ ለዓለመ ዓለም አንትሙኒ እለመነንክሙ ዘንተ ዓለመ ወሐደግሙ ኵሎ ዘብክሙ ወተለውክሙኒ ይከዉን ማሕደርክሙ ውስተ መንግስተ ሰማያት ወትረክቡ ሠናያተ ዘዓይን ኢርእየ ወእዝን ኢሰምዓ ውስተ ልበ ሰብእ ዘኢተሐለየ ኀበ አልቦ ደዌ ወአልቦ ሕማም ወኀዘን ኀበ አሰፈውኩከ

34. ኦ ጴጥሮስ አንተ ወ፲ወ፪ ሐዋርያት እለሐረይኩክሙ አነብረክሙ ዲበ ፲ወ፪ ነገደ እስራኤል ወትፌትሑ ላዕሌሆሙ በከመ ገብሩ።

ይገኛል እነሱ አንተን የሚያምኑ ናቸውና ደጋግ ሰዎችስ እስከ ዳግመኛው መምጫህ ጊዜ የት ይኖራሉ"

32. ጌታዬና መድሐኒቴ ኢየሱስ ክርስቶስ መለሰና እንዲህ አለኝ "ጴጥሮስ ሆይ የመሐይምናንን ማደርያቸው እነግርሃለሁ በኔ ለሚያምኑ መሐይምናን ለጻድቃንና ለነቢያት እንዲሁም ለሌሎች ከዕርገቴ በኂላ ግሩም ወደሆነው መኖርያየ ከሄድኩ በኂላ የንፁሐንንም ማደርያቸው በስሜም አምነው የተጠመቁ ሁሉና ሞት ሳይቀድማቸው ንሥሐ ለገቡ ሁሉ ማደርያቸው የት እንደሆነ እነግርሃለሁ።

33. የኒህ ሁሉ ማደርያቸው ገነት ናት ይህችንም ገነት በኤዶም የተከልኳት ናት በሷም ያርፋሉ እስከ ዘለዓለምም ከዚያው ይሆናል። እናንተም ይህንን ዓለም ንቃችሁ ያላችሁንም ዓለማዊ ንብረት ትታችሁ እኔን የተከተላችሁ አንተም ማደርያችሁ በመንግስተ ሰማያት ይሆናል በሰው ልቦና ያልታሰበ ዓይን ያላየው ጆሮም ያልሰማው ሕመምና ደዌ የሌለበት ሐዘንና ሰቆቃም የራቀበት የደስታን ቦታ ትወርሳላችሁ ይህንንም ላንተ ቃል ገብቻለሁ።

34. ጴጥሮስ ሆይ አንተንና አሥራ አንዱን ሐዋርያት እኔ አስቀድሜ ስለመረጥኩዋችሁ በአሥራ ሁለት ነገደ እሥራኤል ላይ እሾማችሁአለሁ በነሱ ላይም ትፈርዳላችሁ በሥራቸውም

36. ወለካህናት አሐድሮሙ ውስተ አብያተ ብረሃን ወእሬሲ ለለ፩፩ ማሕደር ግሩም በከመ ዕበዮሙ ለቡ እንከ ኦ ጴጥሮስ ብዕልየ ወፀጋየ ዘወሀብኩከ

37. ወአዲ እዌስከከ ኵሎ ዘተሥእልከኒ ኦ ጴጥሮስ አንተ ወሐዋርያት እለሐረይኩክሙ አነብረክሙ ዲበ ነገደ እስራኤል ወትፈትሑ ላእሌሆሙ በከመገብሩ ወለካህናትሰ አሐድሮሙ ውስተ አብያተ ብርሃን ወእሬሲ ማሕደረ በከመ ዕበዮሙ ለቡ እንከ ኦጴጥሮስ ብዕልየ ወጸጋየ ዘወሀብኩከ ወአጸንኦ ወእዌስከከ ኵሎ ዘተሥ እልከኒ ኦ ጴጥሮስ በብዕለፀጋየ ፈጠርክዎሙ ለመላእክትየ ወክብርየ ይዔልሎሙ ወበእለተ ትንሣኤ እሬስዮሙ ለመሐይምናን አለየአምኑ፡ብየ እድ ወአንስት ይኩኑ ንፁሐነ እስመለ እሉ አልቦሙ ነውር ዘአልቦ ሞት ከመ መንፈሳውያን ዘኢየአምሩ ምረራ ለሞት

38. ወእሁቦሙ ዘፈቀዱ ይርአዩ በዓዕይንት ወይስምዑ በአእዛን እምእሳት ዘእንበለ ፍርሃት ኦ ጴጥሮስ አርእየከ ኵሎ ዘይከውን በዕለተ ትንሣኤ ተዓገሥኬ ንስቲተ እስከትበፅሕ ኀበ ዘየዓቢ መዓርግ።

መጠን ፍርድ ታስቀምጡባቸዋላችሁ።

36. ካህናትንም በብርሃን ማደሪያ አሳድራቸዋለሁ ለያንዳንዳቸውም ግሩም ማደሪናያ አዘጋጃለሁ ይህም እንደየትልቅነታቸው ነው ጴጥሮስ ሆይ አንግዲህ አስተውል የሰጠሁህን ብዕሌንና ፀጋዬን የለመንከኝነንም ሁሉ ገና እሠጥሃለሁ እጨምርሃለሁ።

37. ጴጥሮስ ሆይ በፀጋየ ብዕል መላእክትን ፈጠርኩዋቸው የኔም ክብር ይጋርዳቸዋል በዕለተ ትነሣኤም በኔ ለሚያምኑ መሐይምናን ሴቶችና ወንዶች የሞትን ምንነት እንደማያውቁ መንፈሳዉያን ሞትን እንደሌለባቸው ከነውር ሁሉ ንፁሐን ይሆኑ ዘንድ አደርጋቸዋለሁ መሐይምናን በሴቶችና በወንዶች ፆታነት ያሉ ናቸው።

38. የወደዱትንም ያደርጉ ዘንድ መብት እሠጣቸዋለሁ በጆሮቻቸው ይሰሙ ዘንድ የሚሰሙትም ድምፅ ከእሳት የሚወጣ ነው እሳትቱም አይፈሩትም ጴጥሮስ ሆይ በዕለተ ትንሣኤ የሚሆነው አሳይሀለሁ ነገር ግን ወደሚበልጠው ደረጃ እስክትደርስ ድረስ ታገሥ።

39. ኦ ጴጥሮስ ናሁ ይበፅሕ ላዕለ ሕዝብየ ኀዘን ወምንዳቤ እምድሕረ ዕርገትየ ውስተ ሰማይ ወይሰደዱ እስከ አፅናፈ ዓለም ወይመትሩ መለያልዮሙ ወያውእዩዎሙ በእሳት ወያወፅእዎሙ ወባሕቱ አንስ ኢየሐድጎሙ ወአሬእዮሙ ኀይልየ ወመድምምየ ላእሌሆሙ።

40. ኦ ጴጥሮስ ናሁ ተርፈ እምኵናኔ ለዲያብሎስ በሱባዔ ወእምድሕረ ተፈፀመ ሱባዔ ዕቀብ እርኢ መንክራትየ ወፀጋየ ላዕለመሐይምናን እለ የአምኑ ብየ ፩ እምኔሆሙ ይሰድድ ፩ዕልፈ ወ፪ ይሰድድዎሙ ለዕልፍ ወአእላፍ እስከ ያነክሩ ሕዝብ ተአምራትየ ወመንክራትየ ወክብርየ።

41. ኦ ጴጥሮስ ሰበ ዐረጉ ኀበ አቡየ ወነበርኩ በውስተ ስብሐትየ ዘኢዐረቀ አምኔሁ ወእፌኑ ኀቤከ ወንበኵሎሙ አርዳእየ ጰራቅሊጦስሃ ዘይሄሉ።

42. ወኢየሐደገክሙ ወአሐድር ሣህልየ ላዕሌክሙ እስከ ለዓለም ከመትኅዝኑ ኦ ጴጥሮስ አላ ዕቀብ ኵሎ ዘይቤለከ ፈጽም ወደይ ውስተ ልብከ ወለቡ ከመትረክበኒ በመንግሥተ ሰማያት እንዘትሉቅ አንተ።

39. ጴጥሮስ ሆይ እነሆ ወደሰማይ ካረግሁ በኋላ በሕዝቤ ላይ ከፍተኛ መከራ ይደርሳል ከመከራ ብዛት የተነሳም ሕዝቦቼ እስከዓለም ድርቻ ድረስ ይሰደዳሉ በእሳት ይቃጠላሉ አካላታቸው ይቆርጣቸዋል እኔ ግን ከሕዝቦቼ አልለይም ኃይሌንና ተአመራቴን በነሱ ላይ አሳያለሁ።

40. ጴጥሮስ ሆይ ከዲያብሎስ አገዛዝ ሃያ ሱባዔ ይቀራል ይህ የዲያብሎስ አገዛዝ ሲያልፍ በድጋሚ እኔ ለሰው ልጆች የምሠጠውን ጸጋየና መንክራቴ አሳያለሁ ይህንን የኔን ጸጋ የሚጐናፀፉት የኔ መዕምመናን ብዙ ናቸው ከነሱ አንዱ እልፎቹን ያሳድዳቸዋል ሁለቱም ደግሞ አእላፈአእላፋቱን ያሳድዱዋቸዋል ይህንን አስደናቂነገርን የተመለከቱ ሕዝብ ብርሃኔን ተአምራቶቼንና መንኽራቶቼን አይተው ይደነቃሉ።

41. ጴጥሮስ ሆይ ወዳባቴ ባረግሁ ጊዜ ካልተለየሁበት ምስጋናየም በሆንኩ ጊዜ ወዳንተና ወደሁሉም ተማሪዎቼ ለሁል ጊዜ አብሮአችሁ የሚኖርን መንፈስ ቅዱስን እልካለሁ።

42. አልተዋችሁም ይቅርታየም አሳድርባችዋ ለሁ ይህም እስከ ዘለዓለም ነው ጴጥሮስ ሆይ አትዘን የምነግርህንና የምገልፅልህን ሁሉ ጠብቅ እወቅ ወደ ልብህም አስገባው በተሰቀልህም ጊዜ በመንግሥተ ሰማያት እንደምታገኘኝ አስተውል

43. ወኢየሐድገክሙ ወአንድር ሣህልየ ላዕሌክሙ እስከ ለዓለም ኢትኀዝን ኦ ጴጥሮስ አላ ዕቀብ ኵሎ ዘአቤለከ አእምር ወደይ ውስተ ልብከ ወለቡ ከመትረክበኒ በመንግሥተ ሰማያት እንዘሥቁል አንተ ወያዕቆብ ቅቱል ወዮሐንስ ዘሞተ በአፈ አናብስት ወኵሎሙ አርድእት ወኵሎሙ አርድእት ይረክቡ እለቅቱላን በእደጸሮሙ።

44. ኦ ጴጥሮስ ከመ መሐይምናን እለ የአምኑ ብየ ይከውኑ ዝርዋነ ውስተ ኵሉ አሕዛብ ለቡ እንከ ኦ ጴጥሮስ ከመ ትትፍለጥ ሃይማኖቶሙ ለእለየአምኑ ብየ ወየሐውሩ ዘዘዚአሆሙ በቅድመ ብእሲ መሠርይ ሲሞን ዘዕምሕዝበ ዲያብሎስ ዘያሃይድ ሕገ ሲዋናዊ ናሁ አማስና በእንተ ዘተቃረነ ምስሌከ።

45. ወሀለው ሀየ ካልአን እለይትቃረኑ እሉ እሙንቱ ያስደውያን አጥሌም ናባዶን በቶቆዶን አጥሶን ቃርጣን ፍርምና በድሪናን አንናሶ አልማንድዬ መቄዶንያ ጠይጣላና መርቃልስ ሕዝበ ቃጥርያ ሕዝበ ሐናንያ ሕዝበ ለፍንያ ሕዝበ ቀርዶንያ ወዘይመስሎሙ።

46. ወበመዋዕሊሆሙ ይፈደፍድ ረሐብ እምነ ጽጋብ ወይበዝሕ ሞት ውስተ ምድር ኦ ጴጥሮስ ሶበ ተመይጠ ዕጓለአንበሳ ወንብአ ውስተ መካን አእምር ከመ አልፀቀ ጊዜ ሕልቀት

43. የተገደለው ያዕቆብ በአናብስት የተበላው ዮሐንስና አርድእት ሁላቸው በጠላቶቻቸው ተገድለው እኔን ያገኙኛል ተስፍቸውም በመንግሥተ ሰማያት ብዙ ነው።

44. ጴጥሮስ ሆይ በኔ የሚያምኑ ምእመናን እንደሚሉት አስተውል በዚህም ሃይማኖታቸው ለማንም የተለየች ትሆናለች ስለሃይማኖትም ተለያይተው ወደያገሩ ይሰደዳሉ አስቀድሞ በተቃራኒነት ባንተ ላይ ሲሞን መሠርይ ይነሳል እሱም የዲያብሎስን መንገድ ይከተላል ሲሞን በሰይጣናዊ ምግባሩ ሕግን የሚያጠፋ ነው ስለዚህ በተቃራኒነት አንተ ጋር ስለገጠመ አጠፋዋለሁ

45. ከሱም ቀጥሎብዙዎች ተቃራኒዎች ይነሳሉ እነሱም ያስደውያን አጥሌም ናባዶን በቶቆድን አጥሶን ቃርጣን ፍርምና በድሪናን፣ አንናሶ፣ አልማንድዩ፣ መቄዶንያ፣ ጠይጣለን፣ መርቃልደስ፣ የቅጥርያ ሕዝብ የበለፋንያ ሕዝብ የቅርደንያ ሕዝብና ሌሎችንም እነሱም የመሰሉ ያገር ሕዝችን ግለሰቦች ናቸው

46. በዘመናቸው ረሐብ ይፀናል ምግብ አይኖርም በምድርላይም ብዙ ሰዎች ይሞታሉ ጴጥሮስ ሆይ የአንበሳ ደቦል በተመለሰ ጊዜ ወደቦታውም በሄደ ሂዜ ይህን ስታይ የማለቂያ ጊዜ እንደደረሰ

ወእሞከመርኢከ ከመይበዝሕ ሞት ወረሐብ ማዕከለ ነገሥት ዘ፪ዘመዶሙ ወ፪ ማሕበሮሙ ይትቃተሉ በበይናቲሆሙ ለቡኬ ከመ ትማስን ምድር

47. ወይበዝሕ ሕልም መደንግጽ ወያስተርኢ ትእመርተ ሰማይ ውስተ መድር ወአሚሃ ይከውን ቀትል ወዔዋዌ ወእሜጥዎሙ ለሰብእ ውስተ እደመጥባሕት ወአንስ ኢይሰምዕ ጸሎቶሙ ወኢይትዌከፍ ሥእለቶሙ።

48. ወመዋዕሊሁ ለዝ ሕዝብ ዕልወት ይከውን እምኀቤሆሙ ዓቢይ ስደት ወምንዳቤ ላዕለሕዝብ መሐይምናን እለየአምኑ ብየ ወእሙንቱ ይስእሉ ወያንቃዕድው ኀቤየ በፅኑዕ ሥእለት ዘኢኮነ ከማሁ እምትካት ውስተ ዓለም።

49. ሶበሰ ሠዓለ አዳም ወአስተምሐረ ዘከማሁ ሥእለተ እምኢወፅአ እም ውስተ ገነት። አው በመዋዕሊሁ ለኖህ እምኢመፅአ አይኅ ላዕለ ምድር ወለሰብአሰዶምኒ እምኢወረደ እሳት እምሰማይ።

50. አ ጴጥሮስ ንግሮሙ ለሕዝብ ኢይትልው ፍኖቶሙ ለሕዝብ ዕልዋን አለብዎሙ ከመይዕቅው በርትዕት ሃይማኖት። ወሶበ ቆመ በዛቲ ሃይማኖት የሐዩ ለዓለም

እወቅ ተረዳ የሞትን መብዛት ባየህም ጊዜ ረሐብ እንደበዛ ባየህ ጊዜ ሁለት ነገሥታትም እርስበርሳቸው ሲገዳደሉ ባየህ ጊዜ ምድር እንደምትጠፋ ተረዳ።

47. አስደንጋጭ ሕልም ይበዛል የሰማይ ምልክት በዚሁ ምድር ይበዛል በዚሁም ጦርነትና ምርኮ ይበዛል ሰዎችንም ደግሞ ለሞት አሳልፌ እሠጣለሁ እኔም ጸሎታቸውን አልሰማም ልመናቸውንም አልቀበልም።

48. በዚሁ ሕዝብ ጥፋት በነሱ ላይ ከፍተኛ ስደት ይደርሳል ከፍተኛ መከራም ይደርሳቸዋል ይህን ሁሉ መከራ የሚፈጽመው በመሐይምናን ሕዝቤ ላይ ነው። እነሱም ከዚሁ መከራ ለመዳን ወደኔ በማንጋጠጥ ያለቅሳሉ። ይህንንንም ልቅሶና መከራ እጅግ የበዛ ነው ከጥንትም ጀምሮ ያልሆነው ይሆናል።

49. አዳም ዕፀበለስ በልቶ ጥፋት በተቈጠረበት ጊዜ ይህን ያህል ቢለምን ኑሮ ከገነት ባልወጣ ነበር። እንዲሁም በዘመነ ኖኅ የተፈፀመው ጥፋት ከመድረሱ አስቀድሞ ይህን ያህል ምህላ ቢፈፀም ኑሮ ጥፋት ባልደረሰም ነበር የሰዶም ጥፋትም እንዲሁ።

50. ጴጥሮስ ሆይ ሕዝቦችን የካሐዲዎችን መንገድ እንዳይከተሉ ንገራቸው። በቀናች ሃይማኖት ይፀኑ ዘንድም አሳምናቸው ከዚህ ሌላ ግን ከሌላ ክፉ ነገር ርቆና ተጠብቆ በዚች የቀናች

ወይወርስ ብዕለጸጋየ ዘዓይን ኢርእየ ወእዝን ኢሰምዓ ውስተልበሰብእ ዘኢተሐለየ ወአዲዘኢርእዩ መላእክት ወሐይላት።

51. ኦ ጴጥሮስ አሌሶን ለእለይፀንሳ ወየሐፅና በመዋዕሊሆሙ ለሕዝብ። ወእለስ የአምኑ ብየ ይትቀተሉ መብዝሕቶሙ በመጥባሕት ወይኬልሑ አእባን ወአብያተ ክርስቲያናት ወይነፅፉ ማያት ወኢይውሕዙ አፍላግ ወየሐልፍ ወይትመየጥ ዘመን ዓመታት ወይትረስዑ ፀሐይ ወወርህ ወከዋክብት ወይከውን ፅልመት ፫ መዓልተ ወሠለስተ ለያልየ ውስተ ምድር ወይጠፍእ ሠናያት እምሰብእ።

52. ወእምከመበዝሐ ሠናይቶሙ ለሕዝብ ይፈደፍድ እከዮሙ ወትበዝሕ ኃጢአቶሙ ወጌጋዮሙ። ወየሐፅፅ ፍሬ ወፅፀወገዳም ወየሐድሩ አጋንንት ላዕለሰብእ ወይትነሥኡ ሐሳውያን ነቢያት ወአራዊተ ገዳምኒ ይበልዑ ሥጋ ሰብእ ወበእንተ ተፍፃሜተ መዋዕሊሆሙ ይትካፈልዋ ለምድር በሜጥ ወየሐድር ሰብእ ውስተበድው ኅበገዳም ወምድር።

53. ወእምድሕረዝ ይወፅእ በትረመድኅኒት ወሕይወት እምቴማን ወእምዝ ይትቀጠቀጡ እሉ ሕዝብ በውስተ አድባር ናሁ ይመፅእ ንጉሥ እምሥራቅ ከመ ያንቅኅነ

ሃይማኖት የቆመ ሁሉ እስከዘለዓለሙ ይድናል የጸጋየንም ብዕል ይወርሳል። ይህም ዓይን ያላየው ጆሮ ያልሰማው ነው የሰማይ መላእክትም ኃይላትም ያላዩትም ያያል።

51. ጴጥሮስ ሆይ በነዚህ ሰዎች ዘመን ለሚያረግዙና ለሚያሳድጉ ሴቶች ወዮላቸው በዚሁ ዘመን በኔ ከሚያምኑ አብዛኞቹ ይገደላሉ የሚገደሉትም በሠይፍ ነው በዚህ ጊዜ ድንጋዮችና አብያተክርስቲያናት ይጮኻሉ ውሆች ይደርቀሉ ወንዞች ውሃን ማፍሰሳቸው ያቆማሉ እንዲህ እያለ ዘመናትና ዓመታት ያልፋሉ ፀሐይ ጨረቃና ከዋክብት ይረሳሉ ሦስት ቀንና ሦስት ሌሊት ሳያቋርጥ ጨለማ ይሆናል ይህም የሚሆነው በኢየሩሳሌም ዙርያ ባሉት አገሮች ነው በሰዎች ላይ ቂምና ቁጣ ይበዛል። መልካምም ነገር ከሰዎች ይጠፋል።

52. የሰዎች ክፋታቸው ከደግነታቸው ትበልጣለች በደላቸው እጅግ በዝቶ ይታያል። የዱር ዛፍ ፍሬ ይጉድላል አጋንንት በሰዎች ላይ ያድራሉ ሐሰተኞች ነቢያት ይነሳሉ የዱር አውሬዎች የሰውን ሥጋ መብላት ያዘወትራሉ የመጨረሻ ጊዜአቸው ስለሚደርስም ምድርን ተቀራምተው ይከፋፈሏታል።

53. ከዚህ በኋላ የሕይወትና የመድሐኒት በትር ይወጣል (ከቴማን) ከዚህ በኋላ እነዚህ ሕዝቦች በተራራሮች ላይ እያሉ ይቀጠቀጣሉ እነሆ ንጉሥ ከምሥራቅ ይመጣል እሱም

እምንዋም ወይበዝሕ አርማሕ እስከምድር ወይፀንዕ ቀትል ወይከውኑ አብድንት ከመአውግር ወይትሐጐሉ ነፍሳተሰብእ ከመአባግዕ ወአጣሊ።

54. ወትበዝሕ ዓመፃ ወይትከሰት ለደናግል ሐፍረቶን ወይክህድ አብ ወልዶ ወወልድ አባሁ ወገብር እግዚኡ ወወለት እማ ወእም ወለታ ወአግብርት ይትዔበዩ ላዕለ አጋእዝተ፡ሆሙ ወአግአዚት ተሐርፅ ከመ ዓመት ወአዓመትኒ ከመ እግዝእት ወራዙት ይነብሩ መልዕልተ አዕሩግ ወአእሩግ ታሕተ።

55. ወበእንተዝ እሜጥዎሙ ውስተ መፖፃሕት ወይከውኑ መብልዓ ለከለባት ወያንቀለቅል ኀይለሰማያት ወይትቃተሉ ነገሥተ ምድር በበይናቲሆሙ ወይጐይዩ ኵሎሙ ነገሥተ ምድር እምቅድመ ንጉሠ ቴማን። ውእቱሰ ይትቃተል ምስለ ፬ መዓዝነ ዓለም።

56. ወይኴንን ነገሥተ ወይነሥት አብያተ ጣዖት በመዋዕሊሁ ወየአትት ቀትለ ወይሴስል ሐዘን ወኩነኔ እምላዕለሰብእ ወይከውን ዳሕን ወሰላም ወይበዝሕ ፅጋብ ወስተ ምድር ወየሐልፍ እከየመዋዕል ወይመውት ሰብእ አመ ይመፅእ መቅሠፍት ዳግም ዲበምድር ወናሁ እምድሕረዝ ይመፅእ ፍርሐት ወረአድ ወድንጋጼ ዘኢሰማእናሁ እምትካት

የሚመጣው ከእንቅልፍ ያነቃ ዘንድ ነው። የጦርመሣርያ ይበዛል ጦርነትም ይበረታል የሰው አስከሬን በየሜዳው እንደተራራ ይከመራል የሰዎች ነፍሳትም እንደበግና እንደፍየል ይጠፋሉ።

54. በደል ትበዛለች የደናግል ሴቶች ሐፍረት ይገለጣል አባት ልጁን ልጅ አባቱን ይክዳሉ አገልጋይ አሠሪውን ይክዳል እናት ልጇን ልጅ እናቷን ይክዳሉ አገልጋዮች በሐላፊዎች ላይ መታበይን ያሳያሉ እመቤት ትፈጫለች ሠራተኛዋ እንደእመቤት ትሆናለች ወጣቶች ሽማግሎችን ንቀው ከበላይ ይቀመጣሉ ሽማግሎች ደግሞ ከታች ይቀመጣሉ።

55. ለሞትም አሳልፌ እሠጣቸዋለሁ ውሾችም ይበሉዋቸዋል የሰማያት ሐይልም ይነዋወጣል የምድር ነገሥታት እርስበርሳቸው ይገዳደላሉ የምድር ነገሥታት ሁሉ ከቴማን ንጉሥ ፊት መቆም ተስኖአቸው ይሸሻሉ የቴማን ንጉሥ ግን ካራቱ መዓዝነ ዓለም ካሉ ነገሥታት ጋር ይዋጋል።

56. ነገሥታትን ይገዛል የጣዖትንም ቤት ያፈራርሳል ወረትን ያስወግዳን ሐዘን ይወገዳል ተገዥነትም ይወገዳል ድሕነትና ሰላም ይረጋገጣል ጥጋብ ይበዛል በምደር ሁሉ ጥጋብ ይበዛል መጥፎ ጊዜ ያልፋል ሰዎች ግን ዳግም መጥፎ ጊዜ ሊመጣ ይችላል እያሉ በስጋትና በጭንቀት ይዋጣሉ። ፍርሐትና ድንጋጤ ከዚህ ይመጣል የዚሁ ዓይነት ፍርሐትና ድንጋጤ

ወእም ብዝሐፍርሐት ይትሐወክ ነፍስ

57. ወይትነሣእ ቀትል ወይትክዓው ደም ወአእዋፈ ሰማይ ይፀግቡ እምአብድንቲሆሙ ለእለ ተቀትሉ ይበልዑ ወአልቦ ዘይድኅን ዘአንበለ ሕዳጣን ሰብእ ወእለተርፉ ይብሉ ከመዝ ለካልኡ እምአይቴ ብሔር አንተ ወብእሲትኒ ትብል ለካልእታ እምአይቴ ዘመድ አንቲ አብ ይሬኢ ውሉዶ ወውሉድኒ አባሁ።

58. ወኢይት አመኑ በበይናቲሆሙ ወይቀትል ብእሲ ቢፆ ወኢየአምር ካልአ ወእምዝ ይእሕዝዎሙ ለመሐይምናን ወየአሥርዎው እደዊሆሙ በስእርተ ርእሶሙ ወክሳውዲሆሙ በሰናስል ወይወርውዎሙ ውስተአፍላግ ወይ ከልእዎሙ ስትየ ማይ።

59. ወካዕበ ይከውን ዓቢይ ፍርሐት ወታድለቀልቅ ምድር በአሐቲ ዕለት ፫ ጊዜ ወእምዝ ይትነሣእ ዳግመ ንጉሠ ቴማን ዘይመስል ላሕመ ዘያማስን ዘቦ ውስተ ርእሱ አቅርንት።

መቼም ያልታየ ነው። ከሰዎች ፍርሐት ብዛት የተነሳ የነፍስ ነውጥ ይበረታል

57. ጦርነት ይነሳል ብዙ ደም ይፈሳል የሰማይ ወፎች የሰውን በድን በልተው ይጠግባሉ ከጥቂት ሰዎች በቀር የሚድን የለም ከሞት የተረፉት ሰዎች አንዱ ለሌላው ከየት ብሔር ነህ ይለዋል ሴትም ሌላይቱን ጓደኛዋን ከማን ወገን ነሽ ትላታለች አባት ልጁን ይጠብቃል ልጅም አባቱን ይጠብቃል

58. እርስበርሳቸው አይተዋወቁም ወንድ ባልንጀራውን ይገድላል ሌላም ቁም ነገር አያውቅም መሐይማንንም ይይዙዋቸዋል በራሳቸው ጠጉርና በብረት ሰንሰለትም አንገት አንገታቸውን ያስራቸዋል ወደወንዝም እየወረወሩ ይጥሉዋቸዋል ነገር ግን ውሃ እንዳይጠጡ ይከለክሉዋቸዋል

59. በድጋሚ ትልቅ ፍርሐት ይሆናል ምድር ባንድ ዕለት ውስጥ ሦስት ጊዜ ትንቀጠቀጣለች በድጋሚ የቴማን ንጉሥ ይነሳል እሱ ላም ይመስላል ያመነ በራሱ ላይም ሶስት ቀንዶች አሉት

60. ውእቱኬ ያማስን ኵሎ ፍጥረተ በመቅሰፍተ መዓቱ ወይበፅሕ ሀገረ አንተስማ በአልባክ ወይፌፅም በውስቴታ ፍትውቶ በህየ ይማስን ወኢይገብእ ውስተ ብሔሩ እስመ ለሊሁ አዕብየ ርእሶ ውስተ ብሔሩ እስመለሊሁ አዕበየርእሰ ወሐደገ ስብሐተ ፈጣሪሁ ወተመከሐ ወተወደሰ በዕበየ ክብሩ ወሐለየእኩየ

61. ወይቤ አነ በፅንዓኀይልየ ረሰይክዋ ለምድር እስመ በእንተዝ ኮነ ሕጉለ በእዴሁ ለንጉሠ ምሥራቅ ናሁ አማስኖ ወእሬስዮ ሰሀቀ ውስተኵሉ ምድር ወእምድሕረዝ ኦ ጴጥሮስ አእምር ከመእትቤቀላ ወአመዘብራ ለብሔረ ግብጽ ወእነስት ጥቅማ

62. ወእደመስስ ሥረላሕያ ወእምድሕረ ነበረት ብሔረግብፅ ፫ ሱባዔ ወመንፈቀ ሱባኤ ያስተርኢ ተአምር በውስተ ደስያት ወፍርሐት በውስተ ባሕር ወዐቢይ ቀትል ውስተ ቀላየባሕር ወይበውኡ ርኩሳን ሕዝብ ዘመንገለባሕር ውስተ ቤተ መቅደስየ ወያማስኑ አብያተ ክርስቲያናትየ ወያውእዩዎን በእሳት።

63. ወይከይዱ በእገሪሆሙ ትእምረተ መስቀልየ ወይዴግንዎሙ ለመሐይምናንየ ወይቀትልዎሙ በውስተመካን ወእሙንቱ ይዘረው ውስተ ከሉ ምድር

60. እሱ ፍጥረትን ሁሉ ያጠፋል በአልበካ ከተበላችሁ አገርም ይደርሳል በዚችውም አገር የወደደውን ሁሉ ያደርጋል ከዚያ ብዙ ጥፋት ይደርሳል ወደሀገሩም መልሰው ራሱን ከፍ ከፍ አድርጓልና የፈጣሪውንም ምስጋና ትቷልና ትምክህትን በማብዛቱ ራሱ ተመስግኗል ክፋንም አስቧል

61. ከትዕቢቱ ብዛት የተነሳም በኃይሌ ፅናት ምድርን ፈጠርኳት ይላል ከዚህም የተነሳ የጠፋ ይሆናል የሚያጠፋውም የምስራቅ ንጉስ ነው እኔም አጠፋዋለሁ በምድር ሁሉም መዘባበቻ እንዲሆን አደርጋለሁ ጴጥሮስ ሆይ ከዚህ በመቀጠል ጦርነትን አመጣለሁ ግብፅንም እንድትመዘበር አደርጋለሁ ግንቧንም አፈርሳለሁ

62. ደምግባትዋንም እደመስሳለሁ ብሔረ ግብፅ ከተደመሰሰች በኋላ አንድ ተኩል የሱባኤ ጊዜ ቆይቶ በደሴቶች ላይ ተአምራት ይታያል በባሕር ላይ ደግሞ ፍርሐት ይበዛል በባህሩ ዙሪያ የሚኖሩ ርኩሳን ሰዎች ወደቤተ ክርስቲያን ይገባሉ አብያተክርስቲያናትንም በእሳት ያቃጥሉቸዋል።

63. በእግራቸውም ትእምርተ መስቀሌን ይረግጣሉ። መሐይምናንንም ይከተሉዋቸዋል። በዚሁም ቦታ ይገድሉዋቸዋል እነሱ ግን በምድር ሁሉ ይበታተናሉ የዚህ ዓይነት ስደት ከዚህ በፊትም

በከመከነ በመዋዕለ ትካት ወይበዝሕ እኩይ ሕልም ወይከውን ዓቢይ ፍርሐት ውስተኩሉ በሐውርት ወይትዌስክ ዕልዕ ላእዕለመሐይምናን ወአንስ ኢየሐድገክሙ ውስተ ፀፀደፀላዕቶሙ በውእቱ መዋዕል ይፀልሙ ፀሐይ ወወርህ ወይወድቁ ከዋክብት እምሰማይ።

63. ወእምዝ ይመፅእ ንጉሠ ምሥራቅ ወይበዝሕ ቀትል ማእከሌሆሙ ወይነፍሕ ነፋስ ላእለምድር ወይመውቱ ሰብእ ግብፅ በረሐብ ወበብድብድ ወአመፅእ ሞተ ላዕለ ውሉደ አዳም ወያስተርኢ ተአምራትየ በሰማይ።

64. ወእምዝ ያሐውር ንጉሠ ምሥራቅ ብሔረ ግብፅ ወይቀትሎሙ ለእለ ተርፉ ወካዕበ ይቀትሎሙ ለሰብአ ምዕራብ ወይነግሥ ላእለ ኩሉ ምድር ወይትኤዘዙ ሎቱ ኩሉ በሐውርት ወእምብዝሐ ሠራዊቱ ይወርስ ዓበይተ አህጉረ ወይኄንን እምፅንፍ እስከ ፅንፍ ወድምጸ ሠራዊቱ ከመ መንኩራኩር።

65. ወእምግርማሁ ይፀርሑ አውግር ወይትከወስ ኩሉ ኀይለሰማያት ወይከውን ዓቢይ ፍርሐት ወይበክዩ አድባር ወአውግር እምሥራቅ እስከምዕራብ ወእምደቡብ እስከሰሜን።

ታይቷል። መጥፎ ሕልምም ይበዛል። ባገር ሁሉም ትልቅ ፍርሐት ይበዛል በመሐይምናን ላይ ጥላቻ እጅግ ይበዛል። መሐይምናንን ግን በጠላቶቻቸው እጅ እንደወደቁ አልተዋቸውም። በዚሁ ዘመን ፀሐይ ይጨልማል፤ ጨረቃም እንዲሁ። ከዋክብትም ከሰማይ ይወድቃሉ።

63. የምሥራቅ ንጉሥ ከዚህ በኋላ ይመጣል ጦርነትም ይበዛል (በመካከላቸው)። በምድር ላይ ነፋስ ይነፍሳል። የግብፅ ሰዎች ባሰቃቂ ረሐብ ያልቃሉ። የወረርሺኝ በሽታም ከረሐቡ ተከታትሎ ይጨርሳቸዋል በአዳም ልጆች ሞትን አመጣለሁ በሰማይም ተአምራቴን ይታያል።

64. ከዚህ በኋላ የምሥራቅ ንጉሥ ወደግብፅ ይሄዳል የቀሩትንም ሰዎች እንደገና ይገድላቸዋል። በምድር ሁሉም ይነግሳል አገሮች ሁሉም በሱ ሥር በመሆን የሱ ታዛገሮች ይሆናሉ ከሠራዊቱ ብዛት የተነሳም ብዙ ታላላቅ አገሮችን ይወርሳል። ከዳር እስከዳር ሁሉንም ይቈጣጠራል የሠራዊቱም ድምፅ እንደመኪና ይሰማል።

65. ከግርማው አስፈሪነት የተነሳ ኰረብታዎች ይጮኻሉ የሰማያት ኀይልም ይነዋወጣል ታላቅ ፍርሐትም ይሆናል ኰረብታዎችና ተራሮች እንደሰው ያለቅሳሉ ከምሥራቅ እስከምዕራብ ከሰሜን እስከደቡብ ለቅሶ ይሆናል።

66. ወእምድሕረዝ እፌኑ ሣህልየ ወምሕረትየ ላዕለኩሎሙ አሕዛበምድር እስምዕጸሎቶሙ ወስእለቶሙ ለሕዝብየ ለእለ የአምኑ ብየ ወያንቀአድዉ ኀቤየ። ወእለሰ ይትቃረኑኒ አነሥእ ዲቤሆሙ በትረ መቅሠፍትየ ወእቀትሎሙ ወአጠፍኦሙ ወእገብር መድኃኒተ ገሃደ ዲበ ምድር።

67. ወአሬኢ ስብሐትየ ላእለ እለ የአምኑ ብየ ወይገብኡ ሕዝብ በከመትካት ወይትከሰት ኩሉ ዘሕቡእ ወእሬሲ ውስተምድር ምሕረትየ ወአነሥእ እጓለማውታ።

68. ወአነሥእ እጓለአንበሳ ወይሰድዶሙ ለኩሎሙ ነገሥት ወይቀጠቅጦሙ እስመ ሎቱ ወሀብክዎ ሥልጣነ ወከመዝ ተንሥአቱ ለእጓለአንበሳ ከመዘንቃሕ እምንዋም ናሁ ጸላኢ ይወርስ አሐተ ሀገረ ዘመንገለ ምዕራብ እንተመንግሥቱ።

69. ወበእንተዝ በአ ላእሌሁ ቅንአት ለቡኬ ኦ ጴጥሮስ ናሁ ይከውን እምድሕረዕርገትየ ውስተሰማይ ነገሥት ይክሕዱ ስምየ ወይቀትልዎሙ ለኩሎሙ መሐይምናን እለየአምኑ ብየ ዲያብሎስሰ ያነሥኦሙ ለነገሥት ወያፀንዕ ልቦሙ።

66. ከዚህ በኋላ ይቅርታየንና ምሕረቴን በነሱ ላይ (በምድር አህዛብ ሁሉ) እልካለሁ ጸሎታቸውንና ልመናቸውን እሰማለሁ ይህንንም የማደርገው ላመኑብኝ ብቻ ነው። ወደኔ በአንቃዕድዎ ለፀለዩ ሁሉ ይህንን ሁሉ እፈፅምላቸዋለሁ። ለሚቃረኑኝ (ለሚቃወሙኝ) ሁሉ ግን የመቅሰፍቴ በትር አነሳባቸዋለሁ እገድላቸዋለሁ አጠፋቸዋለሁ በግልፅም በምድር ላይ መድሐኒትን አመጣለሁ።

67. ምስጋናየ በሚያምኑ ላይ አሳያለሁ በመከራ ላይ የነበሩትም ሕዝብ እንደቀድሞው ይሆናሉ የተደበቀውም ግልፅ ይሆናል። ምሕረቴንም በምድር ላይ አደርጋለሁ የሙት ልጆችንም አነሳለሁ።

68. የአንበሳ ደቦልን አነሳለሁ ነገሥታትንም ሁሉ ይሰዳቸዋል። ይቀጠቅጣቸውማል እነሱን እንዲቃወም አደርገዋለሁ ሥልጣንም እሠጠዋለሁ። የአንበሳው ደቦል አነሣሥ ከእንቅልፍ እንደመነሳት ያለ ነው በዚሁም አኳያ ከመንግሥቱ ከወደምዕራብ አቅጣጫ ያለውን ቦታ እንዳለ ለመውረስ ይችላል።

69. በዚህም ምክንያት በሱ ላይ ቅንአት አደረበት ጴጥሮስ ሆይ እነሆ ከዕርገቴ በኋላ በሰማይ ላይ ብዙ ሁኔታዎች ይፈጠራሉ ነገሥት ስሜን ይክዳሉ። መሐይምናንም ሁሉ ይገድሉዋቸዋል የሚገደሉት መሐይምናን በስሜ የሚያምኑ ናቸው ነገሥታቱ

70. ወቀዳሚ ዘይትነሣእ እምእሉ ነገሥት ንጉሥ ዘስሙ "ዐ" ውእቱኬ ዘይቀትሉ ለያዕቆብ ረድእየ ዘተሰምየ እኁየ ወእምድሕሬሁ ይትነሣእ ንጉሥ ዘስሙ "ነ" ናሁ ይቀትለከ ኦ ጴጥሮስ ወእምድሕሬሁ ይትነሣእ ንጉሥ ዘስሙ "ጠ" ዘይቀትሎሙ ለአይሁድ።

71. ወይመልሕ ሥሞሙ ወእምድሕሬሁ ይትነሣእ ንጉሥ ዘስሙ "ነ" ወእምድሕሬሁ ይትነሣእ ንጉሥ ዘስሙ "ቀ" ወእምድሕሬሁ ይትነሣእ ንጉሥ ዘስሙ "ከ" ወእምድሕሬሁ ይነግሥ ዘስሙ "ሰ"፣ ዘስሙ "አ"፣ "መ"፣ "ዕ"፣ "ቀ"፣ "ቈ"፣ ዘውእቱ ዘያግሕድ ርትዕተ ሃይማኖተ ወይከ፥ሥት ትእምርተ መስቀልየ።

72. ወይዜከሩ ስምየ ኩሉ ትውልደ ትውልድ እምሥራቀ ፀሐይ እስከ ነዓረብ ወይትባረኩ እምኔሁ ኩሎሙ ነገሥተ ምድር ወይፈትሕ በፅድቅ ወበርትዕ ያፈቅር ፅድቀ ወይፀልእ ዓመፃ ወበመዋዕሊሁ ያስተርኢ ተአምርየ በሰማይ ወበምድር ወያስተርኢ መስቀልየ ለኩሉ ፍጥረት።

ይህን ለማድረግ የሚነሱት ዲያብሉስ ልባቸውን ስለሚያፀና ነው።

70. ከነዚህ ነገሥት አስቀድሞ የሚነሳው "ዐ" ይባላል። ይህም ንጉሥ የኔ ወንድም የሚባለውን ያዕቆብን ይገድለዋል ይህም የዕቆብ የኔ ደቀመዝሙር ነው። ከሱ ቀጥሎ "ነ" የሚባለው ንጉሥ ይነሳል ይህም ንጉሥ አንተን ይገድለሃል። ከሱ በኋላ "ጠ" የሚባለው ንጉሥ ይነሳል ይህ ንጉሥ አይሁድን ይገድላቸዋል።

71. የአይሁድን ሥረመሠረትም ይነቅላል ከሱ ቀጥሎ "ነ" "ሰ" ቀጥሎ "ቀ" "አ" ቀጥሎ "ከ" ከሱ ቀጥሎ "ሰ" ከሱ ቀጥሎ "አ" እንዲሁም መ፣አ፣ዕ፣ቀ፣ቈ በቅደም ተከተል ይነግሳሉ "ቈ" በመጨረሻው የሚነግሰው ሲሆን ይህ ንጉሥ የኔን የቀናች ሀይማኖት ያስፋፋል መስቀሌንም ከተደበቀበት አውጥቶ እንዲታይ ያደርጋል።

72. ስሙንም በትውልደ ትውልድ ሁሉ ከምስራቅ እስከ ምዕራብ ይታወሳል የምድር ነገሥታትም ከሱ ይባረካሉ በፅድቅና በቅንነት ይፈርዳል ጽድቅን ይወዳል ዓመፅንም ይጠላል በዘመኑ የኔ ተአምር በሰማይና በምድር ተአምሬ ይታያል መስቀሌም ለሁሉ ፍጡር ይታያል።

73. ወአንሰ እሄሉ ምስሌሁ ወእሁቦ ኃይለ ወመዊአ ወይበዝኀ መሐይምናን ወይመውኡ ጸላእቶሙ ወእምድሕሬሁ ይነግሡ ነገሥት እለስሞሙ "ከ ር እ ሰ" ወ እምድሕሬሁ ይነግሥ ዘእምዘመዶሙ ዘይቀትሎሙ ለ፪ ነገሥት ዘስሙ "ሰ" ዘይትቃረኖሙ ለመሐይምናን ወበመዋሲሁ ይከውን ስደት ወምንዳቤ፡፡

74. ወእምድሕሬሁ የ፣ወ፣ ይነግሡ ወእምድሕሬሆሙ ይነግሥ ወ እምድሕሆሙ ይነግሥ ዘስሙ‹‹ዋ››ወዝንቱ ንጉሥ ይከውን ሠናየ ወርቱዓ ሃይማኖት ወበመዋዕሊሁ አግህድ ብዙሐ ተአምራትየ ለዕለ የአምኑ በትንሣኤየ፡፡

75. ወእምዝ ይነግሥ ‹‹መ›› ወውእቱ ይከውን ቡሩከ በርትዕት ሃይማኖት ወይፈትሕ በፅድቅ ወበርትዕ ወአነሂ እሄሉ ምስሌሁ ወእምድሕሬሁ ይነግሥ ‹‹ሰ››ወይከውን ቡሩከ ወንፁሐ ከመእም ቅድማሁ

76. ወእምድሕሬሁ ይነግሥ ‹‹ር›› ወውእቱ ይከውን ከሐዴ ወዓላዌ ትእዛዝየ ዘያበጥል ህግየ ወሥርዓትየ ዘሥዩም ላዕለ እስክንድርያ ወእምድሕሬሁ ይነግሡ ነ፣ሰ፣ጠ፣ሀ፣

73. እኔም ከሱ ጋር እኖራለሁ ኃይልንና አቸናፊነትንም አስጠዋለሁ መሐይምናን ይበዛሉ፡፡ ጠላቶቻቸውንም ያቸንፋሉ ከዚሁ ቀጥሎም "ከ፣ ር፣እ፣ ሰ" የሚባሉ ነገሥታት ያነግሳሉ ከዚያ በመቀጠል ግን ከነሱ ወገን የሆነ "ሰ" የሚባል ይነግሣል እሱም ሁለቱን ነገሥታት ይገድላቸዋል መሐይምናንንም ይቃወማቸዋል በዚሁ ዘመን ስደትና መከራ ይሆናል፡፡

74. ከሱ በመቀጠል የወ›› ይነግሳልሉ ከነሱ በኃላ ደግሞ ‹‹ዋ›› የሚባል ይነግሳል እሱ የተባረከና የተመረጠ ይሆናል ሃይማኖቱም የቀና ደግ ይሆናል በሱ ዘመን ብዙ ተአምራቶቼንና ድንቅ ሥራዎቼን አሳያለሁ የማሳየውም ለሚያምኑብኝ ነው፡፡

75. እሱም ደግ የተባረከ በቀናች ሃይማኖት የሚሄድ በፅድቅና በቅንነት የሚፈርድ ይሆናል እኔም በሕይወቱ ሁሉ ከሱ አልለይም ከሱ በመቀጠልም ‹‹ሰ››በመባል የሚጠራ ንጉሥ ይነግሣል ይህም ንጉሥ እንደበፊቱ ደግ ይሆናል፡፡

76. ከሱ ቀጥሎ ‹‹ር›› በመባል የሚጠራ ንጉሥ ይነግሣል ይህ ንጉሥ ከሐዲና የእሥክንድርያን ሕግንና ሥርዓትን የሚያጠፋ ይሆናል ከሱ በበመቀጠልም ነ፣ሰ፣ጠ፣ሀ፣ ይነግሣሉ ከሐዲዎች ናቸው፡፡

77. ወእምድሕረዝ ይነግሥ ‹‹ሀ››ዘውእቱ ህርቃል ደሐሪ ዘይከውን እምቅድመ መዓትየ ወያፀርዕ ርትዕተ ሃይማኖተ ወበመዋዕሊሁ ያስተርኢ ካልእ ሕገ ዘኢኮነ ሠናየ ከመ ዲያብሎስ ወበእንተዝ ዕልወ ንጉሠ እፌኑ መዓትየ ላእለሕዝብየ ወእዘብጦሙ በበትረ መቅሰፍትየ

78. ወአማስኖሙ በአራዊተ ገዳም እምገፀ ምድር ወአውየው ከመ አንሥርት ደቂቀ ዕልዋን ወመናፍቃን ትዝምደ አፍያት ሕዝበ ዓመፃ በላዕያነ ሥጋ ሰብእ እመራር ትውልድ እለ ይክዕው ደመ ትጉሃን ለኵሉ እኩይ ወርኵስ መፍቀርያነ በሊዕ ወሥታይ። ይትሜክሁ ወይፀልዑ ጽድቀ አዕርክተ አጋንንት መስተቃትላነ ላዕለ ስምየ ወላዕለኵሎሙ እለ የአምኑ ብየ መፍቀርያነ ዓመፃ ወጸላእያነ ርትዕ አብዳን ነባብያን በአፉሆሙ ተላውያነ ቤተ ጣዖት መሠርያን ወቤተ ሰዶም ወትዝምደ ጋኔን መደልዋን ለገፀ ሰብእ እለ የአብዩ ርእሶሙ።

79. ኦ ጴጥሮስ ሕዝብየ እምኢክህሉ ገቢረ ዘንተ ለእመ ኮነ ዝንቱ ሕዝብ ያብርዎሙ ለሰብእ በመጣብሕ ይትመየጡ ውስተ ሕጎሙ ዘእንበለ ቀዲሙ ወበመዋዕሊሁ ለዝ ሕዝብ ይከውን ዓቢይ ድለቅልቅ ወድንጋጼ።

77. ከሱ በመቀጠል ‹‹ሀ›› የሚባል የሱም ሙሉ ስም ‹‹ሀርቃል›› የሚባል ይነግሣል እሱም ለኔ መዓት የተጋለጠ የቀናችንም ሃይማኖት ለማጥፋት ሆን ብሎ የሚነሳ ነው በዘመኑ ከርጉም ዲያብሉስ የመነጨ እጅግ የተጠላ ህግ ይታያል በዚህም ከሐዲ ንጉሥ ምክንያት በሕዝቦቼ ላይ መዓቴን እልካለሁ በመቅሰፍቴ በትርም እመታቸዋለሁ።

78. እንደአሞራዎች ያለ ጥፍር ባላቸው የዱር አውሬዎች አጠፋቸዋለሁ እነሱ የከሐዲዎች ልጆችና የመናፍቃን ልጆች ናቸው የእፍኝት ልጆችም የዓመፅ ልጆችም ይባላሉ የሰውን ሥጋ የሚበሉ ናቸው የመራራው ልጅ ውጤቶች ናቸው የረከሰውንና የከፋውን ሥጋ ለመብላት ብቻ ይተጋሉ በመብልና በመጠጥ ጊዜአቸውን ያሳልፋሉ።

79. ጴጥሮስ ሆይ ሰዎች መጥፎውን ሥራ እንዲሠሩ ባያስገድዱዋቸው ኑሮ ይህንን ሁሉ ለመፈፀም ባልተገደዱም ነበር በመግደልና በማንገላታት ሌሎች ሰዎች የነሱን ፈቃድ እንዲፈፅሙ ያደርጋሉ በዚሁ ሕዝብ ዘመን ከባድ ነውጥና ድንጋጤ ይከሰታል።

80. ወሕዝብ ይሬስዩ ጽልዓ ምስለኵሉ ሕዝብ ወይላፅዩ ርእሶሙ ወየዓጥቁ ሐቋሆሙ ወይትሜሰሉ በካልእ ፍጥረት ወያሠርግው ርእሶሙ ወሥጋሆሙ ወይትሬስዩ ከመ አጋንንት ወአነ አወፅኦሙ ለሕዝብ እምብሔር ኀበ ተወልዱ።

81. ወእፌንዎሙ ውስ ተከሉ መካነ እምዕራብ እስከ ምሥራቅ እምሰሜን እስከ ደቡብ ወያመዘብሩ ብዙሐ አሕጉረ ወትበፅሕ መንግሥቶሙ እስከ ባሕረመምለኪያነ ጠዖት ወይነሥቱ አብያተ ነገሥት ወይገብሩ ቀትለ በኵለሄ ወራዙቶሙ ለሕዝብ።

82. ወደቂቆሙ ይፀልዕዎሙ ወይዛለፍዎሙ አእሩግ ኢየአምኑ ዘእንበለ ሐፍረት እስመ አልቦሙ ምሕረት ወልድ ይፈቅድ ቀቲለ አቡሁ ወአብኒ ቀቲለወልዱ ዘእንበለርትዕ።

83. እሉ ሕዝብ ይበረብሩ አብያተ ክርስቲያናት ወይነሥኡ ንዋየ ወርቅ ወቡሩር ወያንሕሉ መሠረታቲሆሙ ለእለ ተሐንፁ በስምየ ወለእለ የአምኑ በስምየ ይመትሩ አንፎሙ ወእዘኒሆሙ ወየዓውሩ አዕይንቲሆሙ ወይመትሩ እደዊሆሙ ወእገሪሆሙ ወያማስኑ ነፍሳተ ብዙሐነ

80. ሕዝቦች ከሕዝቦች ጋር ይጣላሉ ራሳቸውን ይላጫሉ ወገባቸውንም ይታጠቃሉ ከዚህም የተነሳ በሚፈፅሙት ቅጥ ያጣ አካሄድ ሌላ ፍጡር መሰለው ይታያሉ የገዛ ሥጋቸውንም በመሸላለም ልዩ ፍጡር ለመምሰል ይጥራሉ እንደ አጋንንት ይሆናሉ እኔም ከተወለዱበት አገር አስወጥቼ ወደሌላ እንዲባረሩ አደርጋለሁ።

81. በምዕራብ እስከምስራቅ ከሰሜን እስከ ደቡብ ባሉት ቦታዎች ሁሉም ይበታተናሉ በየደረሱበትም አገር ሁሉ ብዙ አገሮችን ያጠፋሉ የነሱም መንግሥት ጣዖትን እስከሚያመልኩ አገሮች ይደርሳል የነገሥታትን ቤቶች ለማፍረስ የተዘጋጁ ይሆናሉ በየቀኑም ጦርነትን ይቀሰቅሳሉ ይህንንም የሚፈፅሙት ወጣቶቻቸው ናቸው።

82. ልጆች ወላጆቻቸውን ይጣላሉ ሽማግሌዎችንም ይዘልፋሉ የሚሳደቡትና የሚሰደቡት ሽማግሌዎች ሃይማኖተኞች ናቸው ሲሳደቡም ሐፍረትና ፍርሐት አይሰማቸውም ልጅ አባቱን አባት ልጁን ያለፍርሐት ይገድላል።

83. እነዚህ ሕዝቦች አብያተክርስቲያናትን ይበረብራሉ ከወርቅና ከብር የተሠራ ንብረትንም ይወስዳሉ በናስም የታነፁትንም አብያተክርስቲያን ያፈርሳሉ መሠረቶቻቸውንም ይነቅላሉ እኔን የሚያምኑትንም ምእመናን አፋቸውን ጆሮቻቸውንም እጆቻቸውንና እግሮቻቸውን ይቆርጣሉ በዚህም የረከሰ ተግባር

ዘአንበለ ምሕረት ወያማስኑ አድያመ በመዓቶሙ::

84\. ወእነሥእ እጓለአንበሳ ወይሰድዶሙ ለኲለሙ ነገሥት ወይቀጠቅጦሙ እስመሎቱ ወሀብክዎ ሥልጣነ ወከመዝ ተንሥኦቱ ለእጓለ አንበሳ ከመ ዘንቃሕ እምንዋም ናሁ እለሂ ይወርሱ አሐተ ሀገረ ዘመን ገለ ምዕራብ እንተ መንግሥት::

85\. ወበእንተዝ ቦአ ላእሌሁ ቅንአት ለቡኬ "ኦ" ጴጥሮስ ናሁ ይከውን እምድሕረ ዕርገትየ ውስተሰማይ ነገሥት ይክሕዱ ስምየ ወይቀትልዎሙ ለኲሎሙ መሐይምናን እለ የአምኑ ብየ ዲያብሎስ ሰ ይነሥኦሙ ለነገሥት ወያፀንዕ ልቦሙ::

86\. ወቀዳሚ ዘይትነሣእ እምእሉ ነገሥት ንጉሥ ዘስሙ ‹‹ዐ›› ውእቱኬ ዘይቀትሎ ለያዕቆብ ረድእየ ዘተሰምየ እኁየ ወእምድሕሬሁ ይትነሣ እንጉሥ ዘስሙ ‹‹ነ›› ወእምድሕሬሁ ይትነሣእ ንጉሥ ዘስሙ ‹‹ቀ››ወእምድሬሁ ይትነሣእ ንጉሥ ዘስሙ ‹‹ከ›› ወእመድሕሬረሁ ይነግሥ

የብዙሐንን ነፍሳት ለማጥፋት የተሠለፉ ይሆናሉ ምሕረትና ርሕራሄ በነሱ ዘንድ ፈፅሞ የለም በመዓታቸውም አገሮቻውን ያጠፍሉ::

84\. የአንበሳ ዶቦልን አነሳለሁ ነገሥታትንም ሁሉ ይሰዳቸዋል ይቀጠቅጣቸዋል እነሱን እንዲቃወም አደርገዋለሁ ሥልጣንም እሠጠዋለሁ የአንበሳውን ዶቦል አነዚሥ ከእንቅልፍ እንደመነሳት ያለ ነው በዚሁም አኳያ ከመንግሥቱ ከወደምዕራብ አቅጣጫ ያለውን ቦታ እንዳለ ለመውረስ ይችላል::

85\. በዚህም ምክንያት በሱ ላይ ቅንአት አደረበት ጴጥሮስ ሆይ እነሆ ከዕርገቴ በኃላ በሰማይ ላይ ብዙ ሁኔታዎች ይፈጠራሉ ነገሥት ስሜን ይክዳሉ መሐይምናንም ሁሉ ይገድሉዋቸዋል የሚገደሉት መሐይምናን በስሜ የሚያምኑ ናቸው ነገሥታቱ ይህን ለማድረግ የሚነሱት ደያብሎስ ልባቸውን ስለሚያፀና ነው::

86\. ከነዚህ ነገሥት አስቀድሞ የሚነሳው "ዐ" ይባላል ይህም ንጉሥ የኔን ወንድም የሚባለውን የዕቆብን ይገድለዋል ይህም ያዕቆብ የኔ ደቀመዝሙር ነው ከሱ ቀጥሎ‹‹ነ›› የሚባለው ንጉሥ ይነሳል ይህ ንጉሥ አይሁድን ይገድላቸዋል። ከሱ ቀጥሎ ‹‹ነ›› ‹‹ከነ›› ከጥሎ "ቀ" አ"ቀ" ቀጥሎ "ከ" ከሱ ቀጥሎ

ዘስሙ ‹‹ሰ›› ፤ ዘስሙ ‹‹አ›› ዘስሙ ‹‹መ›› ዘስሙ ‹‹አ›› ‹‹መ››፤ ‹‹ዐ››፤ ‹‹ቀ››፤ ‹‹ቁ››፤ ዘውእቱ ዘያግሕድ ርትዕተ ሃይማኖተ ወይከሥት ትእምርተ መስቀልየ።

87. ወይዜከሩ ስሞኩሉ ትውልደ ትውልድ እምሥራቀፀሐይ እስከነዓረብ ወይትባረኩ እምኔሁ ከሎሙ ነገሥተ ምድር ወይፈትሕ በዕድቅ ወበርትዕ ያፈቅር ዕድቀ ወይፀልእ ዓመፃ ወበመዋዕሊሁ ያስተርኢ ተአምርየ በሰማይ ወበምድር ወያስተርኢ መስቀል ለኩሉ ፍጥረት።

88. ወአንሰ እሄሉ ምስሌሁ ወእሁቦ ኃይለ ወመዊአ ወይበዝኅ መሐይምናን ወይመውኡ ፀላእቶሙ ወእምድሕሬሁ ይነግሡ ነገሥት እለስሞሙ ከ ር እ ስ ወእምድሕሬሁ ይነግሥ ዘእምዘመዶሙ ዘይቀትሎሙ ለ፪ ነገሥት ዘስሙ "ሰ" ዘይትቃረኖሙ ለመሐይምናን ወበመዋዕሊሁ ይከውን ስደት ወምንዳቤ።

89. ወእምድሕሬሁ "የ፤ወ፤ ይነግሡ ወእምድሕሬሆሙ ይነግሥ ዘስሙ "ዋ" ወዝንቱ ንጉሥ ይከውን ሕሩየ ወርቱዓ ኀይማኖት ወበመዋዕሊሁ አግህድ ብዙሐ ተአምራትየ ለእለየአምኑ ትንሣኤየ።

"ሰ" ከሱ ቀጥሎ "አ" እንዲሁም መ፤አ፤ ዐ፤ቀ፤ቁ፤ በቅደም ተከተል ይነግሳሉ "ቁ" በመጨረሻም የሚነገሰው ሲሆን ይህ ንጉሥ የኔን የቀናች ሀይማኖት ያስፋፋል መስቀሌንም ከተደበቀበት አውጥቶ እንዲታይ ያደርጋል።

87. ስሙንም በትውልደ ትውልድ ሁሉ ከምስራቅ እስከ ምዕራብ ይታወሳል የምድር ነገሥታትም ከሱ ይባረካሉ በዕድቅና በቅንነት ይፈርዳል ጽድቅን ይወዳል ዓመፅንም ይጠላል በዘመኑ የኔ ተአምር ይታያል ተአምር በሰማይና በምድር ተአምሬ ይታያል መስቀል ለሁሉ ፍጡር ይታያል።

88. እኔም ከሱ ጋር እኖራለሁ ኃይልንና አቸናፊነትንም እሰጠዋለሁ መሐይምናን ይበዛሉ ጠላቶቻቸውንም ያቸንፋሉ። ከዚሁ ቀጥሎም "ከ፤ር፤እ፤ስ" የሚባሉ ነገሥታት ይነግሳሉ ከዚህ በመቀጠል ግን ከነሱ ወገን የሆነ "ሰ" የሚባል ይነግሣል እሱም ሁለቱን ነገሥታት ይገድላቸዋል መሐይምናንንም ይቃወማቸዋል በዚህ ዘመን ስደትና መከራ ይሆናል።

89. ከሱ በመቀጠል "የ፤ወ" ይነግሳሉ ከነሱ በኋላ ደግሞ "ዋ" የሚባል ይነግሳል እሱ የተባረከና የተመረጠ ይሆናል ሃይማኖቱም የቀና ደግ ይሆናል በሱ ዘመንም ብዙ ተአምራቶቼንና ድንቅ ሥራዎቼን አሳያለው።የማሳየውም ለሚያምኑብኝ ነው።

90. ወእምዝ ይነግሥ "መ" ወውእቱ ይከውን ቡሩክ በርትዕት ሃይማኖት ወይፌትሕ በጽድቅ ወበርትዕ ወአነሂ እሄሉ ምስሌሁ ወእምድሕሬሁ ይነግሥ "ላ" ወይከውን ቡሩከ ወንፁሐ ከመ እምቅድሜሁ፡፡

91. ወእምድሕሬሁ ይነግሥ "ር" ወውእቱ ይከውን ከሐዲ ወአላዊ ትእዛዝ ዘያበጥል ሕገ ወሥርዓተ ዘሥዩም ላእለ እስክንድርያ ወእምድሕሬሁ ይነግሱ "ነ፣ሰ፣ጠ፣ሀ"፡፡

92. ወበውእቶን መዋዕል ይትነሥኡ ሕዝብ ላእለሕዝብ ወነገሥት ላእለ ነገሥት ወሠራዊት ላእለሠራዊት ወይሴስል ፍቅር እምኔሆሙ ወውእተጊዜ ያንቀዓድው መሐይምናን ወይፀርሑ ኀቤየ ወአንሰ ኢይሰምዕ ጸሎቶሙ በእንተ እበየ ምግባሮሙ፡፡

93. ወሕዝብ ይከርዩ መቃብረ ወያወፅኡ አዕፅምተ ሙታን እለተቀትሉ በመዋዕለ ኖኅ ዘሐለወ እስከመዋዕሊሆሙ ወይረግዙ በአርማህ አልባሰሰብእ ወይከውኑ በመዋዕሊሆሙ አዕፅምቲሆሙ ለሰብእ ዝርዋነ ዲበምድር ከመዘርአ ገራሕት፡፡

94. ወይፈርሑ እምኔሆሙ ኲሉ አህጉር እለይነብሩ ሐይቀ ባሕር ወእምፍርሐቶሙ ይሠጠማ አሕማር ወይከይድዎን

90. ከዚሁ በኋላ ለ"መ" ይነግሣል በእሱም ደግ የተባረከ በቀናች ሃይማኖት የሚሄድ በዕድቅና በቅንነት የሚፈርድ ይሆናል እኔም በሕይወቱ ሁሉ ከሱ አልለይም ከሱ በመቀጠልም "ለ" በመባል የሚጠራ ንጉሥ ይነግሣል ይህም ንጉሥ እንደበፊቱ ደግ ይሆናል፡፡

91. ከሱ ቀጥሎ "ር" በመባል የሚጠራ ንጉሥ ይነግሣል ይህ ንጉሥ ከሐዲና የእሥክንድርያን ህግንና ሥርዓትን የሚያጠፋ ይሆናል ከሱ በመቀጠል "ነ፣ሰ፣ጠ፣ሀ፣" ይነግሳሉ ከሐዲዎችም ናቸው፡፡

92. በነዚህ ዘመናት ሕዝቦች በሕዝቦች ላይ ይነሳሉ ነገሥትም በነገሥታት ላይ ይነሳሉ በሠራዊት ላይም ሠራዊት ይነሳሉ ከነሱም ዘንድ ፍቅር ትርቃለች በዚህም ጊዜ መሐይምናን በእንቃዕድዎ ይቆማሉ ወደኔም ይጮኸሉ እኔም ፀሎታቸውን አልሰማም ክፍዎች ናቸውና፡፡

93. ሕዝቦችም መቃብርን እየቆፈሩ በኖህ ዘመን ሙተው የተቀበሩትን ሰዎች ዓፅምን ያወጣሉ ቆፍረው የሚያወጡትም እስከዘመናቸው ተጠብቆ የኖረውን ነው የሰዎችንም ልብሶች በያዙት ጦር ይወጋሉ በዘመናቸው የሰዎች አጥንት በምድር ላይ የተዘሩ የእሕል ዘር መስሎ በምድር ሁሉ ይበተናል፡፡

94. በያገሩ ያሉትም ሕዝቦች ይፈሩአቸዋል በባሕር ጠረፍ ያሉት ሁሉ እነሱን ይፈራሉ እነሱን ከመፍራት የተነሳም

በእገሪሆሙ ወይበልዑ ተመርተ አልቦ ዘይክል ከሊዓፍ ትወቶሙ ወየሐንፁ ዘተመዝበረ ወያመዘብሩ ዘተሐንፀ ወይሬስዩ ምሕዋረ ፍኖት በድወ ወኵሉ ትምክህቶሙ በላዕዮ ርእስ ወበአሠንዮ ዕፅፍ ወበተሠርግዎ አልባስ።

95. በሠራዊቶሙ የዓግትዋ ለኢየሩሳለም ወይወርሱ አድያሚሃ እምዕራብ እስከምሥራቅ ወካዕበ ይፌኑ ሠራዊተ ካልእመንግሥት ነበ ምዕራብ እስከ ምስራቅ ወይወርስ ኵሎ መንግሥታተ ምድር ወያስተጋብእ ውስተ እዴሁ።

96. ወእምዝ የሐውር ኢየሩሳሌም ወየሐንፅ ዘተመዝበረ ወያነሥእ ጥቅማ ወይወርስ አድያሚሃ ኦ ጴጥሮስ አሚሃ ይትፌስሑ ኵሎሙ መሐይምናን እለየአምኑ ብየ ናሁ ያውዕዩዋ ለደማስቆ ወይነሥቱ መሠረታቲሃ በእንተ እከዮሙ ለእለይነብሩ ውስቴታ።

97. ወእምዝ ይትመየጥ ውስተሀገረ መንግሥቱ በዓቢይ ፍሥሐ ወሐሴት ወይነብር ዲበ መንበረ መንግሥቱ ብዙኃ ዓመታተ እስመ ውእቱ ይገብር ትእዛዝየ ምስለ መሐይምናን እለ የአምኑ ብየ ፪ ሱባዔ ወንጉሥሰ ይከውን መድሐኒቶሙ ለመሐይምናን በእዴሁ።

መርከቦች ይሠጥማሉ እነሱም መርከቦቹን በእግራቸው ይረግጡአቸዋል የሚበሉትም (ምግባቸው) የተምር ፍሬ ነው የፈለጉትን ቢሠሩ ሊከለክላቸው የሚደፍር የለም የተገነባውን ያፍርሳሉ የፈረሰውንም ያንፃሉ የምድረበዳንም መሄጃ ያበጃሉ ትምክሕታቸው ራስን በመላጨት ይገልፁታል በልብስም ይገልፁታል።

95. በዘመናቸው ኢየሩሳሌምን ይከቧታል አውራጃዎቿንና አካባቢዋንም ይወርሳሉ የሚወርዋትም ከምሥራቅ እስከ ምዕራብ ያለው ክፍል ነው እንደገና ሌላው መንግሥት ከምዕራብ እስከ ምሥራቅ ያለውን ለመያዝ ሠራዊቱን ያዘምታል ብዙ ቦታዎችንም በቁጥጥሩ ያስገባል።

97. ከዚህ በኋላ ወደኢየሩሳሌም ይሄዳል የፈረሰውንም ሠርቶ ግንቡን ከፍ ያደርጋል አውራጃዎቿንም ይወርሳል ጴጥሮስ ሆይ ያንጊዜ መሐይምናን ሁላቸው ይደሰታሉ መሐይምናኑ በኔ እምነት ይኖራሉ እነሆ ደማስቆንም ያቃጥሏታል መሠረቶቿንም ይነቃቅላል በነዋሪዎቿ ጥፋት ይደርሳል

97. ከዚያ በኋላ ወደ ቀድሞው የመንግሥቱ አገር ይመለሳል የሚመለሰውም እየተደሰተ ነው በመንበረመንግሥቱም ብዙ ዓመታትን ያሳልፋል እሱ ትዕዛዜን የደርጋልና እኔም ከሚያምኑ ሰዎች ጋርም ሌሎችን ይቃወማል በዚሁም ለሁለት ሱባኤ ይቆያል በእጁም ያድናቸዋል።

98. ወናሁ ይእሕዝዎ ለዕልው ሕዝብ ዘንቤ ቀዳሚ ወንትቤቀሎሙ ምክብዒተ ህየንተ ዘገብሩ እኩየ ላእለመሐይምናን ወያሜክሩ ኵሎ ፍጥረተ እምእንጋለ አንበሳ እስመ ይቤሉ ሞት ኢይመፅእ ኀቤነ።

99. ወእምአሜሃ ኢይፀውሩ ደቂቀዕልዋን ንዋየ ሐቅል ወይትሐነፅ ሀገር ዘመዝበረ ወይትፌስሑ መሐይምናን እለየአመኑ ብየ ፍሥሐ ዘኢየሐልቅ ለቡኬ ኦ ጴጥሮስ ከመይከውን ዝንቱ ኩሉ እምቅድመ ዳግም ምፅአትየ ውስተ ዓለም ፳ወ፪ ሱባዔ ወመንፈቀ ሱባዔ ሠዳጥ።

100. ኦ ጴጥሮስ ናሁ ከሰትኩ ለከ ኵሎ ዘይከውን በደሐሪ መዋዕል ወረሰይኩ መንግሥታተ ኵሎ ዓለመ በአምሳለ ፬ ራእይ አሐዱ ገፀ ንሥር ወካልኡ ገፀ አራዊት።

101. ወሣልሱ ነምር ወራብዑ ገጸ አንበሳ ዘይፀንሳ እምስሉ አራዊት ቀዳሚ ዘይሰመይ ገፀ ንሥር ንጉሠ ባቢሎን ውእቱ ወካልኡ ይመስል ገፀ አርዌ ንጉሠ ደቂቀ ኤልድዮስ ወሣልሱ ዘይ መስል ገፀነምር ንጉሠ ዩናናውያን ወራብዑ ዘይመስል ገፀ አንበሳ ንጉሠ ሮም ዘየዓቢ ወይከብር እምኵሎሙ ነገሥት።

102. ይነግሥ ንጉሠ ባቢሎን ፳፻ ወንጉሠ ደቂቀ ኤልድዮስ

98. ከዚያ በመቀጠል እነሆ አስቀድመን የጠቀስነውን ጥፋተኛ ሕዝብ ይዙታል እኛም በመሐይምናን ላይ ክፉ ስለሠሩ ዕጥፍ ድርብ አድርገን እንበቀላቸዋለን ከአንበሳ ደቦል ስለተፈፀመው ይህ ነገር ፍጥረታት ሁሉ ያደንቃሉ ሞት ወደኛ አይመጣም ይላሉና

99. ከዚህ ጊዜ ጀምሮ የሕግ ተላላፊዎች ልጆች የጦር መሣሪያ አይሸከሙም የጠፋው አገር ይቀናል እኔም የሚሞት መሐይምናን ደስ ይሰኛሉ ደስታቸውም አያልቅም ጴጥሮስ ሆይ አስተውል ይህ ሁሉ የሚሆነው ወደዚህ ዓለም ከመምጣቴ አስቀድሞ ሰባሁለት ሱባኤና ግማሽ ሱባኤ ካለፈ በኋላ ነው

100. ጴጥሮስ ሆይ እነሆ በሌላ ዘመን የሚሆነውን ሁሉ ከገለፅኩልህ በዓለም ሁሉም መንግሥታትን ሾምኩህ እነዚህም ነገስታት አንዱ በአራቱ አምሳያ ሆኖ አንዱ የንሥር ገፅ ይኖረዋል ሁለተኛው ደግሞ የአውሬ መልክ ይኖረዋል።

101. ሶስተኛው በነብር ይመሰላል ከፍተኛው በአንበሳ ይመሰላል አንበሳ ከአራዊት ሁሉ ይጠነክራል በንሥር የተመሰለው የመጀመሪያው የባቢሎን ንጉሥ ነው በአውሬ ፊት የተመሰለው ሁለተኛው የኢልድዮስ ልጆች ንጉሥ ነው በነብር የተመሰለው የዮናናውያን ንጉሥ ነው በአንበሳ የተመሰለውና አራተኛው ከሁሉ የበላይ የሆነው የሮም ንጉሥ ነው እሱም ከነገስታት ሁሉ ይበልጣል

102. የባቢሎን ንጉሥ ለአምስት መቶ ዓመት ያህል ይነግሣል

ይነግሥ በትልቁ አመት አሰብ ወንጉሠ ዮናናውያን ይነግሥ ፫ ኃምስተ መጠነ መንፈቀ መንግሥቶሙ ለደቂቀ ኤልድዮስ

103. ንጉሠ ሮምስ ይነግሥ እስከ ለዓለም ወእስከ ዳግም ምጽአትየ እምነ ጉሠኤልድዮስ ይወፅኡ ፲ወ፪ነገሥት እለይፈትሑ ፍትሐ ወፅድቀ ወእምድሕረ እሉ ይወፅኡ ፪ ነገሥት ንኡሳን ወይነግሡ በመዋዕሊሆሙ ሕዳጠ ወይፈትሁ ፬ በማእከለ ምድር ወለ፬ እምኔሆሙ ትፀንዕ መንግሥቶሙ፡፡

104. ወይተርፉ ፫ ነገሥት ዘእምአሐዱ ዘመድ ቀዳሚ እምእሉ ነገሥት ይትቀተል በውስተአራት ወዳግም ይነግሥ ፩ ዓመተ ወመንፈቀ ዓመት ወሣልስ ይከውን እኩየ ወየሐውር በፍትወተ ነፍሱ ወኢይትዌከፍ ምክረ ሰብእ ወይትረሰይ ውስተ ቀትል ለሊሁ ወይፈትሕ እስ ከ፪አፍላግ ምስለ ሠራዊቱ፡፡

105. ወይቀትል ብዙኃነ ሕዝበ ወእምዝ የሐውር ወይበውእ ሶርያ ወየዓውድ በድወ ወእምዝ የሐውር ወየሐሥሥ ሀገረ ፈረንሳዊያን ወይቀትልዎ በማዕከለ አድባር ወለእሉ ፲ወ፪ ነገሥት ቀዳሚ ዘይነግሥ እምኔሆሙ ዘስሙ "ሮ"

የኤልድዮስ ልጆች ንጉስ በበኩሉ በአሰብ አቆጣጠር መጠን ይነግሣል የዮኖናውያን ንጉሥ ደግሞ ሶስት ጊዜ አምስት ሱባዔን ይነግሣል

103. የሮም ንጉሥ ግን እስከ ዘለዓለም እስከ ዳግም መምጫዬ ጊዜ ድረስ ይቆያል ከኤልድዮስ ልጆች ንጉሥ አሥራሁለት ነገሥታት ይወጣሉ ከነዚህ ነገሥታት ትክክለኛውን ፍርድ በእውነት ይፈርዳሉ ከነሱ በኋላ ሁለት ንኡሳን ነገሥታት ይነግሳሉ ዕድሜያቸው ጥቂት ነው ሁለታቸው በምድር ማሐል ይጠፋሉ ከነሱ ይልቅ የአራቱ ነገሥታት መንግሥት ትፀናለች

104. ሦስቱ ነገሥታት ብቻቸውን ይቀራሉ ሦስቱ አንድ ነገድ ናቸውና አንደኛው በአልጋው ላይ እያለ ይገደላል ሁለተኛው ቀጥሎ ላንድ ዓመት ተመንፈቅ ይነግሳል ሶስተኛው ክፉ ይሆናል በራሱም ፍላጐት ብቻ ይመራል የሰውን ምክር አይቀበልም ራሱ ጦርነትን ይቀሰቅሳል ከሠራዊቱ ጋርም እስከ ሁለቱ ወንዞች ይደርሳል

105. ከዚህ ጊዜ ጀምሮ ያልፋል ወደ ሶርያ ይገባል ምድረበዳውንም ይዞረዋል ብዙ ሕዝብንም ይገድላል እንደገና ተመልሶ ወደ ሶርያ ይገባል ምድረ በዳውንም ለሁለተኛ ጊዜ ይዞረዋል ባለበትም የፋርሳውያንን አገር አስሶ ያገኛል በዚህ ጊዜ በሁለቱ ተራሮች መካከል ፋርሳውያን ይገድሉታል ከዚያ በመቀጠል ቀደም ብለው ከተጠቀሱት አሥራሁለት መካከል አንድና "ሮ"

106. ወበመዋዕሊሁ ይተልው ሕዝብ ድሕሬሁ ወየሐውሩ በፍናዊሁ ወይገብር ሕገ ወሥርዓቶ ወእምድሕሬሁ ዘስሙ "ዕ" ይነግሥ ወይወርስ አሕጉረ በተኬንዎ ወበፍቅር ወያፈቅሮሙ ለመሐይምናን ወለእለ የአምኑ በየ ወየዓቅቡ ኪዳንየ ዘለዓለም ዘምስሌሆሙ።

107. ወእምድሕሬሁ ይነግሥ ዘሰሙ "መ" ዘይወርስ ብሔረ ደርባጋን ወበቀዳሚት ይትሜሰል ከመ ዘይፈትሕ በጽድቅ ወበርትዕ ወእንተ ውስጡ ምሉእ ዓመፃ ወሐይድ ወእምድሕሬሁ ይነግሥ ዘስሙ "ዓ" ዘየዐፅድ ዘኢዘርአ ወያስተጋብእ ዘኢኮነ ዘዚአሁ

## ምዕራፍ ፰ ትምህርተ ኖላዊ ዘተፈነወ እምኀበ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ለጴጥሮስ ወእምኀበ ጴጥሮስ ለቀሌሚንጦስ ወም ሥጢራቲሁ

1. በስመ አብ ወወልድ ወመንፈስቅዱስ ፩ አምላክ ንፅሕፍ ኀይለ ወንቀድም ተአምረ ዘአርአዮ እግዚአብሔር

የሚባል ይነግሣል

106. በሱ ዘመን ሕዝብ ይከተሉታል እሱ በሚጓዝበት መንገድም ይጓዛል ህጉንና ሥርዓቱንም ይፈፅማሉ ከሱ ቀጥሎ "ዕ" በሚል ፊደል ስሙ የሚጀምረው ንጉሥ ይነግሣል ይህ ንጉሥ ብዙ አገሮችን ይቆጣጠራል አገሮቹን የሚቆጣጠረው በእርቅ በፍቅርና በሰላም ነው በኔ የሚያምኑትን መሐይምናን ያፈቅራቸዋል እነሱ የኔን ቃል ኪዳን ይጠብቃሉ።

107. ከዚያ ቀጥሎ የሚነግሰው "መ" በሚለው ፊደል የሚጠራው ነው ይህ ንጉሥ ደርባን በመባል የምትታወቀውን አገር ይቆጣጠራል እሱ ለመዠመሪያ ጊዜ በፅድቅና በቅንነት የሚፈርድ መስሎ ይታያል ውስጡ ግን ቀማኝነትንና ውንብድናን የተሞላ ነው ከዛም ቀጥሎ "ዓ" በሚል ፊደል ስም ይነግሣል እሱም ያልዘራውን የሚያጭድ የራሱ ያልሆነውን የሚሰበስብ ነው።

## ምዕራፍ ስምንት ከጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ለጴጥሮስ ከጴጥሮስ ለቀሌ ሚንጦስ የተነገረ መልእክትና ምሥጢሮቹ

1. በአብ ወወልድ በመንፈስ ቅዱስ ስም አንድ አምላክ እግዚአብሔር ለቅዱስ ጴጥሮስ የገለፀለትን ተአምር አስቀድመን እንፅፋለን

ለጴጥሮስ

2. ርእሰ ሐዋርያት ዓዋዲ፣ መጋቢ መንግሥተ ሰማያት ዘተወፈየ እምኀበ ሊቁ መራኁተ ዘጽድቅ ከመ ይፍታሕ ወያርኁ ወያብእ ዘፈቀደ ለዘይደልዎ በጽድቅ ወበርትዕ፡፡

3. ወካዕበ ለዘኢይደልዎ ይዕፁ ውስተ ገፁ ዕንቀፀ ዘመንግሥተ ሰማያት ወእምድሕረ ተንሥአ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ እምነ ምውታን በሣልስት ዕለት ወበመለኮቱ መሐረነ ምሥጢረ መንግሥተ ሰማያት፡፡

4. ወነፍሐ ላእሌነ መንፈስ ቅዱስ ዘወፅአ እምኀበ አቡሁ ንንሣእ ንሕነ ቀዲመነ፡፡ ወእምዝ ነሐብ በበፆታሁ ቀዳሚ ሊቃነ ጳጳሳት ወእመንቱኒ ይፀግው ለካህናት ወለዲያቆናት፡፡ ወሶበ አልፀቀ ለዕርገት ውስተ ሰማያት ዐረግነ ውስተ ደብረ ዘይት ወአርአየነ ኵሎ ተእምረ ወመንክረ እምጥንቱ እስከተፍጻሜቱ፡፡

5. ወዘከመፈጠረ ኵሎ ዓለመ በቃሉ ወበኪነጥበቡ ወካዕበ አርአየነ ኵሎ ፍጥረቶሙ ወነፍሶሙ ለዓለም በውስተ ዕራቱ ወካዕበ ዳግመ ምዕአቶ ወዘከመይትሌለዩ ሐጥአን እምፃድቃን በመንግሥተ ሰማያት ወዘከመይዴየኑ ኃጥአን ውስተኵነኔ ነደ እሳት፡፡

2. ይህ ጴጥሮስ የመንግሥተ ሰማያትን ሥልጣን የተረከበ ከሊቀካህናት ክርስቶስም ለመንግሥተ ሰማያት ዝግጁዎች የሆኑትን ያስገባ ዘንድ ቁልፍ የተረከበ የሐዋርያት መጋቢ ነው፡፡

3. በድጋሚም መንግሥተ ሰማያት እንዳይገባ ለሚገባው (ከመንግሥተ ሰማያት እንዲርቅ ለሚገባው) የመከልከል ሥልጣን ተሠጠው ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከሙታን ተነስቶ በመለኮቱ የመንግሥተ ሰማያትን ምሥጢር አስተምሮናል፡፡

4. በኛ ላይም መንፈስ ቅዱስን እፍ አለብን ይህ መንፈስ ቅዱስ ከአብ የወጣ ነው እኛም እሱን ተቀበልን እኛም በየደረጃው ይህንን (መንፈስ ቅዱስን) በቅድምያ ለሊቃነጳጳሳት እንድናስተላልፍ ሥልጣን ተሠጠን እነሱም ለካህናትና ለዲያቆናት እንዲያስተላልፉ ሥልጣን ተሠጣቸው የጌታችን ዕርገት በደረሰ ጊዜ ወደደብረዘይት ወጣን ተአምራትንም ሁሉ ለማየት ቻልን፡፡

5. ጌታችን በመለኮቱ ዓለምን እንዴት እንደፈጠረ (በቃሉና በኪነጥበቡ)፡፡ በዓለም ያሉትንም ፍጡራን ነፍሳቸው በመዳፉ እንደሆነች አሳየን፡፡ ስለዳግም ምፅአቱ ምሥጢርም አሳየን ሐጢአተኞች ከፃድቃን እንዴት እንደሚለዩ (በመንግሥተ ሰማያት) አሳየን ሐጢአተኞች ወደኩነኔ ቦታ እንዴት

6. ወዘንተ ኵሎ መሐረነ ወአርአየነ ወአጥበበነ እስከ መልአ ልባቢነ ወይቤለነ እመቦ ዘተገድፈ ብክሙ እምነዘነገርኩክሙ ብዙሐ ተአምራተ ወመንክራተ እምዘርኢክሙ ወሰማዕክሙ ሶበዓረገ አነ ሶቤሃ ይመፅእ ጰራቅሊጦስ፡፡ መንፈሰ ዕድቅ ዘይፌኑ አቡየ ለክሙ፡፡

7. ወውእቱ ያዜክረክሙ ወያሌብወክሙ ወያፀንዓክሙ ለገቢረፈቃድየ ወለዓቂበትእዛዝየ፡፡

8. ኦ ወልድየ ቀሌሚንጦስ በከመአንተ ይእዜ ተስእልከኒ ሊተ አነ አሜሃ ተስእልዎ ለእግዚእየ ወአምላኪየ ወእቤሎ አለብወኒ ኵሎ እግዚኦ ኵሎ ዘከመእኤዝዞሙ ለሊቃነ ቤተክርስቲያን ወኵሎ ሥርዓተ፡፡ ወአውሥአኒ ወይቤለኒ ዑቅ ወለቡ ዘከመነገርኩከ ወአንተኒ ኢትንግር ለባእድ ለእለ አልቦሙ አእምሮ ወልቡና ወይከውን ነገርየ ስላቀ በኀቤሆሙ ወያገብኡ ቃልየ ድሕሬሆሙ ኢትክስት ነገርየ፡፡

9. ዘንተ ለእለአልቦሙ አእምሮ ወልቡና ዘእንበለ ለጳጳሳት ወለኤጲስ ቆጶሳት እለ ተሐርዩ እምሕዝብ ወኮነ ቅሱመ ቃሎሙ በደመመለኮት ወያነሥእዎ ለዘወድቀ እምድቀቱ እምእመ ወድቀ በኀጢአት ውስተ መልዕልተ ጽድቅ

እንደሚጣሉም አሳየን፡፡

6. ጌታችን ኢየሱስክርስቶስ ይህንን ሁሉ አስተማረን፤ አሳየን፤ አእምሮአችን ከፈተልን፤ ልቡናችን እስኪሞላ ድረስ፡፡ እንዲህም አለን "እኔ ከገለፅኩላችሁ ሁሉ የሚዘነጋችሁ ካለ ካያችሁትም ተአምራትና መንክራትና ከሰማችሁትም ሁሉ የምትዘነጉት ካለ እኔ ካረግሁ በኂላ አባቴ ወደናንተ የሚልከው መንፈስ ቅዱስ ወደናንተ ይመጣል፡፡

7. ይህ መንፈስ ቅዱስ የተረሳውን ሁሉ ያስታውሳቹኂል ፈቃዴንም ትጠብቁ ዘንድና ፈቃዴን ታደርጉ ዘንድ ያጠናቹኂል፡፡

8. ልጄ ቀሌሚንጦስ ሆይ ዛሬ አንተ እኔን እንደጠየቅኸኝ እኔም በጊዜው ለአምላኪየና ለመድሐኒቴ ጠየቅሁት እንዲህም አልኩት "የቤተክርስቲያንን መሪዎች ሥርዓትን የሚጠብቁበት እንዴት ልዘዛቸው በማለት ጠየቅሁት እሱም መለሰና እንዲህ አለኝ "ጥንቃቄ ማድረግ አለብህ ምሥጢራትን ሁሉ አስተዋይ አእምሮ ለሌላቸው አትግለጥ ለነሱ ከነገርካቸው ቃሌን መዘባበቻ ያደርጉታል ስለዚህ ለማን ምሥጢራትን መግለጥ እንዳለብህ እወቅ ተረዳ፡፡

9. ይህንን ታላቅ ምሥጢር ለጳጳሳትና ለኤጲስ ቆጶሳት ካልሆነ በቀር አእምሮ ለሌላቸው አትንገር ጳጳሳቱ በሕዝብ ተመርጠው የቀረቡ ናቸውና ቃላቸው በመለኮት ጨው የተጣፈጠ ነው ኃጢአተኛውን ከወደቀበት የሐጢአት ዓዘቅት ወደፅድቅ

በንሥሐ።

10. ወኢይኩን ክሡተ ዝንቱ ነገር ለእለኢየዓቅቡ ወኢይገብሩ ትእዛዝየ ወቃልየ ዘወፅአ እምአፉየ። ወእለሰ የዓብዩ ዘንተ ትእዛዝየ ዓላውያን እሙንቱ ኵሎሙ ኃጥአንአምድር ወርጉማን ኵሎሙ እለይትገሐሱ እምትእዛዝየ ዝንቱሰ ነገር ይከውን ምሥጢረ ፈድፋደ።

11. እስመ ክቡር ወሕቡእ ዘእነግረከ ይእዜ ወኢይሬእያ ሰውብ ወዘኢኮነ ንፁሐ ወዘማ ወርኩሰ ወዘያሰግር ወያጣው ወዘያሐትት ማርያነ ወሐረሳውያነ እመሂ በኮከብ አው በመጽሐፍ።

12. እመሂ በነደ፣ እሳት እመሂ በባሕር አው በአፍላግ ወእመሂ በዕቅፍተእግር አው በንቃወአራዊት አው በይምን አው በፅግም እመሂ በአብሕርት አው በበድው እመሂ ዘያረኩስ ሥጋሁ በእንስሳ ወበአራዊት እመሂ በተባዕት ከመ ዘምስለ አንስት።

13. እመሂ ዘይትዌከል ልብሰ ዘኢተውህበ ሎቱ እመሂ ጓሕላዊ ዘይሠርቅ ንዋየቢፁ ወእመሂ በሐሰት ዓማፄ ቢጹ ወሃያዴ ንዋየ ባእድ ወተአጋሊ ወእመሂ ሐሳዊ ወመፀብሐዊ ወፈታውያነ ለእኩይ ወእለየሐውሩዎሙ ለእለ ያበዝኑ ተኬንዎ ለእኩይ ወእለ ይሌቅሑ ወርቆሙ በርዴ ወእለ ይነሥኡ ሕልያነ እምላእለንፁሐ እሎንተ ኵሎሙ

በንሥሐ ጉትተው ያወጡታል።

10. ትእዛዜን ለማይጠብቁና ለማይቀበሉ ይህ ምሥጢር ተገልጦ አይነገር ይህ ምሥጢር ከአፌ የወጣ ነውና እነዚያ ትእዛዜን የማይቀበሉ ሁሉ ወንጀለኞች ናቸው። ሁሉም የምድር ሐጢአተኞች የተረገሙ ናቸው። ስለዚህ ከትእዛዜ የራቁ ይሆናሉ። ይህ ምሥጢር እጅግ የተጠበቀ ይሆናል።

11. ይህ የምነግርህ ምሥጢር ክቡርና የተደበቀ ነው። ንፅሕና የሌለው ሰው አያየውም ዘማዊ የረከሰ የሚያስጠነቁል ጠንቋዮችን የሚከተል በኮከብና በሌላም የሚያሟርትም አያየውም።

12. በወፍ የሚያሟርት በእሳት በባሕር በወንዝ፣ በእግር እንቅፋት፣ በአውሬ ጩኸት፣ በግራ ወይም በቀኝ በባሕሮችም ቢሆን በምድረ በዳም ቢሆን፣ ሥጋውን በእንስሳና በአራዊት፣ በምድረበዳ እንዲሁም በተለያየ መንገድ እኔ የምጠላውን ሁሉ የሚፈፅም አምልኮተ ባእድንም የሚፈፅም አይኑር።

13 ለሱ ያልተሠጠውን ልብስ ለመልበስ የሚጓጓ፣ በሌብነት የሚኖር ዓመፀኛ ቀማኛ ትግሉን በመጥፎ አካሄድ ያደረገ የሌላውን ሐብት የሚመኝ ቀረፅ የሚቀበል ክፋትን መሥራትና መናገር የሚያዘወትር መጥፎ ነገርን ለመሥራት የሚራቀቁትን ሰዎች የሚከተል ገንዘቡን በአራጣ የሚያበድር ከሰው ይህን አስፈፅምልሀለሁ እያለ ጉቦን የሚቀበል እነዚህን የመሳሰሉት

አስቈረረት ነፍስየ።

14. ወለእለይገብርዎ ለዝንቱ ርሑቃን እምግብር ወየሐይው ቦቱ ኢይሰምዕዎ ለዝንቱ ቃልየ ወኢይረስይዋ ለዛቲ መፅሐፍ ከመ ኢይሳለቁ ወኢይትቃፀኡ በዓዕይንቲሆሙ ከመ ኢይትመዓዖሙ በጊዜሃ ወኢያጥፍኦሙ እስመ እትመዓዕ ፈድፋደ በላእለ እለ ይትዔወርዎ ለቃልየ።

15. ወእመሰ ቦ ዘይብል እምእለ የሐውሩ በዛቲ ምግባር እስከ ዮም ኢሰማዕኩ ከመዝ ቃላተ ወሶበ ሰማዕኩ ትካት ዘንተ እምንእስየ ከመዝ እምኢያማስንኩ ሥጋየ ወእምኢያቃለምኩ ነፍስየ።

16. ወለእመ ደንገፀት ነፍሱ ወበከየ በሐዘን ወነሥሐ እምጌጋዩ እትአደዋ ለንጢአቱ እስመ አነ እግዚአብሔር መኀኪሁ ወለኀኵሁ ወመጋቢሁ ወአቃቢሁ ወመሴስይ ለኵሉ ዘሥጋ። አነ እንተ እፍአሁ ወአነ እንተ ውስጡ ለኵሉ ዘሥጋ እነድቅ በደቂቅ ወአሐንፅ ወአፁፅ ወእጠቀልል በረቂቅ ወእነሥእ በድኩም ወአስተጋብእ በስፉሕ ወእዘሩ ከመሐመድ ወእለጉም በግሩም ወአኅጽጽ በበንስቲት።

17. አረውፆ ለመብረቅ ወእመይጦ በቅፅበት አበርሕ ልጐታተ ወእከሥት ቀላያተ ወአንጐደጕድ በላእሉ ወአድለቀልቅ

ሁሉ እፀየፋቸዋለሁ።

14. ይህን የረከሰ ተግባር የሚፈፅሙ በዚሁም ሕይወታቸው የሚመሩ ቃሌን አይሰሙም ይህቺንም መፅሐፍ የነሱን የመዘባበቻና መጠቃቀሻ ሊያደርጉዋት አይገባም ይህን ከፈፀሙ ወድያው የቁጣየን በትር እንዳላኅርፍባቸው ይጠንቀቁ ላጠፋቸውም እችላለሁ ቃሌን ችላ በሚሉ ሰዎች ላይ ቁጣዬ ይበዛል።

15. ከነዚህ በመጥፎ ሥራ ተሠልፈው ከሚኖሩ መካከል ይህንን የመሰሉ የተግሳፅን ቃላት ብሰማ ኑሮ ቀድሞውኑ ለጥፋት ሥጋየንና ነፍሴን በክፉ ነገር ባላበላሽሁ ነበር የሚል ካለ ግን።

16. ነፍሱም ስለደነገጠች በልቅሶና በሐዘን ከተጸጸተ ሐጢአቱን እሠርዝለታለሁ። እኔ እግዚአብሔር ይቅርባይና ፈጣሪ ሁሉን ለመመገብ የምችል ነኝ ሁሉንም የምጠብቅና ሁሉንም የምመግብ እኔ ብቻ ነኝ በውስጥም ይሁን በውጭ ሥጋ ለባሽ የሆነውን ሁሉ በየጥቂቱ ሰውን እገነባዋለሁ። በፍጥነትም አሳድገዋለሁ። በረቀቀ አኳኋን አለመልመዋለሁ በደከመ አካልም አነሳዋለሁ በሰፊው እሰበስበዋለሁ እንደትብያ እበትናለሁ በአስደናቂ ሁኔታም እዘጋለሁ።

17. መብረቅን አሮጠዋለሁ በቅፅበትም እመልሰዋለሁ የባሕር ውስጥ ዋሻውንም አበራዋለሁ ጥልቅ ውሆችንም እገልፃለሁ።

በታሕቱ መሠረታተ ወአሐውኮ ለአንበሪ በውስተምንባሪሁ።

18. ወአኀሥሮ ለዕቡይ በሐይለ መዋቅሕቲሁ ወእፈትሖ ለንሱሕ እመዋቅሕቲሁ ወአሌዕሎ ለትሑት ወአሐሥሮ ለዕቡይ ወእሁብ ሥርየተ ለዘይኔስሕ እማዕምቀልቡ። ወአንተሰ ንግሮሙ ፈቲነከ ልቦሙ ለጳጳሳት ወሊቃነጳጳሳት ከመኢይክስትዎ ለዝንቱ ነገር ለእለ አልቦሙ ልቡና።

19. ከመኢይትመዓዕ ላእሌከ ወላእለእለከማከ ሰበ ተሳለቅዎ ለነገርየ ወለቃልየ ዘወፅአ እምአፉየ እስመ ይጥዕሞሙ ምግባረኀጢአቶሙ ወይመርሮሙ ምግባረጽድቅ።

20. ወለእለሰ ያፈቅሩኒ ይጥዕሞሙ ቃልየ እመዓር ወሶከር ወይትበደር እምአእላፍ ወርቅ ወብሩር እስመ ክቡር ቃልየ በኀበ እለያፈቅሩኒ ወየዓቅቡ ትእዛዝየ ወአነ አፈቅሮሙ ፈድፋደ ወእሄሉ ዘልፈ ምስሌሆሙ ወአዲ ህግየ ምስሌሆሙ ውስተ ልቦሙ አሌብዎሙ ወአሰምዖሙ ቃልየ በውስተ ሕሊና ሆሙ።

21. ወመንፈሱ ለአቡየ ይትዋቀስ ሎሙ በኵሉ ዘነበቡ

ከበታቹን አነዋውጠዋለሁ መሠረቱን እንዲንቀጠቀጥ አደርጋለሁ። አሣውንም ካለበት እንዲጨነቅ አደርጋለሁ።

18. ትዕቢተኛውን አሥረዋለሁ በሠንሰለቴ አሥረዋለሁ ንሥሐ ለገባ ከታሠረበት እፈታዋለሁ የበታች ሁኖ የኖረውን አነሳዋለሁ ትዕቢተኛውን አዋርደዋለሁ ንሥሐ ለሚገባም ሥርየትን እሰጠዋለሁ አንተም ጳጳሳትና ሊቃነጳጳሳት ይህንን ሊቀበሉ የሚችሉትን አስተዋዮች እየመረመሩ እንዲገልፁላቸው ንገራቸው።

19. ይህን በፍጥነት ካላስተላለፍክ ባንተ ላይና አንተን በመሰሉ ሁሉ መዓት ሊወርድ ይችላል ቃሌንና ነገሬን መሳለቂያ የሚያደርጉ ሰዎች እንዳይኖሩ አስተውል። ለክፉዎች መልካም ሥራን መሥራት ይመራቸዋል የሐጢአትን ሥራ መሥራት ደግሞ ይጥማቸዋል።

20. ለሚወዱኝ ግን ቃሌ ይጥማቸዋል ከማርና ከሱኳር በበለጠም ይጣፍጣቸዋል ከብዙ እልፍ ወርቅና ብርም ይመረጣል በሚወዱኝ ዘንድ ቃሌ የከበረ ነው ትእዛዜን በሚያከብሩም ዘንድ የከበረ ነው። እኔም ዘወትር ከነሱ አልለይም የኔም ህግ በልባቸው አሥርፀው ከነሱ ጋር ይዘውት ይገኛሉ እኔም ልቡናቸው በርቶ እኔን በቀና መንፈስ እንዲከተሉኝ ልቡናቸውን አበራለሁ በሕሊናቸው ቃሌን አሰማቸዋለሁ።

21. ያባቴ መንፈስም በተናገሩት ሁሉ ይናገርላቸዋል በወንጌል

በከመይቤ በወንጌል፡፡ እስመመንፈስ ኅበፈቀደ ይነፍሕ ወቃሎ ትሰምዕ ወኢየአምር ኅበየሐውር ወኅበይወፅእ፡፡ ወከማሁ ይከውኖ መንፈስ ቅዱስ ለዘያፈቅር ቃልየ ወይገብር ትእዛዝየ፡፡ ወእለሰ ይፀልውኒ ወይፀልእዎ ለቃልየ ወኢይገብሩ ትእዛዝየ ይወፅእ እምኔሆሙ መንፈስ አቡየ፡፡

22. ወይበውእ ላእሌሆሙ መንፈስ ዲያብሎስ ውእቱኬ ዘይሜሕሮሙ ምግባረ እኩይ በዘይገብሩ በከመ ነገርኩከ ቀዲሙ፡፡ እስመ ኢይትኤረይ መንፈስ ቅዱስ ምስለዲያብሎስ ወአልቦሙ ሥንዐ ማእከሎሙ ወለእ ለይገብሩ ምግባረ ዲያብሎስ ይትኴነኑ ምስሌሁ ውስተ ገሀነም ወእለሰ ይገብሩ ምግባረ መንፈስቅዱስ ይትፌሥሑ ውስተ ገነተ ትፍሥሕት፡፡

23. አንተሰ ንግሮሙ ለሥዩማነቤትየ ከመ ይግበሩ ትእዛዝየ ወይዕቀቡ ሕግየ ወሥርዓትየ፡፡

24. ወከመ ይኩንዎሙ አርአያ ለሕዝብ ለምግባረጽድቅ እንዘየዓቅቡ ርእሶሙ እምዝሙት በእደዊሆሙ ከመ ኢይግበሩ ወበአዕይንቲሆሙ ከመኢይርአዩ ከንቶ ወኢይስምዑ ነገረ ሐሱመ፡፡

25. አላ ያንፅሑ ርእሶሙ ወእደዊሆሙ ከመኢይትረከብ

"መንፈስ ወደፈቀደው ይነፍሳል ድምፁን አይሰማም የት እንደሚገባና እንደሚወጣም አይታወቅም" የሚል ተፅፏል እንደዚሁ ሁሉ ቃሌን ለሚያከብር መንፈስቅዱስ ይጠብቀዋል፡፡ እኔን ለሚጠሉና ቃሌንም ለሚጠሉ እንደዚሁም ትእዛዜን ለማይፈፅሙ የአባቴ መንፈስ አይጠጋቸውም ከነሱ ይርቃል እንጂ፡፡

22. የዲያብሎስም መንፈስ ያድርባቸዋል እሱም የረከሰ መንፈስ ሁኖ መጥፎ ሥራን ያሠራቸዋል ይህም አስቀድሜ እንደነገርኩህ የዘወትር ሥራቸው ይሆናል፡፡ መንፈስቅዱስ ከዲያብሎስ ሥራ ጋር አይገናኝምና በመካከላቸውም ስምምነት የለም የዲየብሎስን ሥራ የሚሠሩ ከዲያብሎስ ጋር ይኰነናሉ የመንፈስ ቅዱስን ሥራ የሚሠሩ ደግሞ ከሞት በኋላ በዓፀደ ነፍስ ሲደሰቱ ይኖራሉ፡፡

23. አንተ ግን የቤቱን ሹማምንት ሕጌን እንዲጠብቁ ሥርዓቴን እንዲያከብሩ ንገራቸው፡፡

24. እነሱ ለተከታዮቼ ምዕመናን መልካሙን አርአያ ማስተላለፍ አለባቸው፡፡ እነሱን በመመልከት ምዕመናን የፅድቅን ሥራ ሊሠሩ ይችላሉ፡፡ ከዝሙትም ይጠበቃሉ በእጃቸው መጥፎውን እንዳይነኩ በዓይናቸው መጥፎትን እንዳያዩ መጥፎም ነገር እንዳይሰሙም ይሆናሉ፡፡

25. ከዚሁም ለመራቅ ራሳቸውን ንፁሕ ያድርጉ፡፡ ምንም ይሁን

በላዕሌሆሙ ነውር ወኢበምንት ምግባረ ኃጢአት ከመኢይበሉ አሕዛብ ኀበእግዚአብሔር አምላኮሙ።

26. ወሶበሰ ኢያፍቀርዎ እምኢአቀቡ ትእዛዞ ወእምኢገብሩ ዘንተ በከመገብሩ ካህናት ደቂቀ እሥራኤል በውእቱ መዋዕል እግዚአብሔርሃ ኢይፈርሁ ወለጣኦታት ይሠግዱ። ወይበሉሙ ፩ እምነቢያቲሆሙ በእንተአክሙ አሕዛብ ይፀርፉ ላእለስመ እግዚአብሔር።

27. አዝዞሙ ከመይዕቀቡ ሕግየ ወትእዛዝየ ወይሁሩ በሥርዓትየ በከመሆርክሙ አንትሙ አርዳእየ በትእዛዝየ ወኢትንሣእ ፍጡነ ዘእንበለ ትጠይቅ ሕይወቶ ከመኢትኩን ንሱሐ ላእለዘሐለፈ ግብርከ ወሐቲተከ ወጠይቅ ከመኢይኩን እንተአውፅኡ ላእሌነ ነውረ ወነገረሐፍረት።

28. እምብእሲ ድንግል ወእም ድንግል ብእሲት ይትወለድ ብፁእ ብእሲ ወእም ሕድግት ወዘማ ኢይትወለድ ሠናይ ብእሲ በከመ ሙሴ ወአሮን እለአቀቡ ሕግየ።

29. (ሀ) ወከማሆሙ ካህናት ያንጽሑ እለአልቦሙ ነውር ወኢስብረተ ወኢፅርዓተ ወኢዕቁበ አው የማናይ አው ፀጋማይ ወኢምቱረ ዕዝን ወኢ ላዕለአ ልሳን።

ምን አስነዋሪ ምግባርን እንዳይፈፅሙ ይሁኑ ከኃጢአት ሥራ ሁሉ ይራቁ ይህ ከሆነ ከእግዚአብሔር አምላካቸሙ ዘንድ ይገባሉ።

26. የእግዚአብሐር አምላካቸውን ትእዛዝ ባልቻሉም ነበር ይህንን ባያደርጉ የእሥራኤል ካህናት እንኳ ከመጥፎ ተግባር ለመጠበቅ አልቻሉም የእግዚአብጠርን ትእዛዝ አፍርሰው ለጣዖት የሰገዱበት ጊዜ አለ ከዚህም የተነሳ ከነቢያቶቻቸው አንዱ ስለነሱ ጥፋት "አሕዛብ የናንተን መጥፎነት አይተው በእግዚአብሔር ስም ላይ ይሳደባሉ" ብሏቸዋል።

27. ትእዛዜን ይጠብቁ ዘንድ ሕጌንና ሥርዓቴንም ይጠብቁ ዘንድ እዘዛቸው እናንተ ተማሪዎቼ ትእዛዜን እንደጠበቃችሁ እንዲሁ ይሆናል። ማንንም ነገር ሳትመረምርና ሳትጠነቀቅ በችኮላ አንድን ነገር አትሥራ በችኮላ አንድን ነገር ለመሥራት ከሞከርክ ተመልሶ ነቀፋንና ውርደትን ያስከትልብሃል።

28. ከድንግል ሰው ና ከድንግል ሴት የተመረጠ ሰው ይወለዳል ከአመንዝራ ሴትና ወንድ ግን መልካም ሰው አይወለድም እንደአሮንና እንደሙሴም ትእዛዜን የሚጠብቅ አይወለድም።

29. (ሀ) እንዲሁ ንፁሐን ካህናቶቼ ነውር የሌላቸው ይሁኑ ስባሪ ጉድለት ቀኝምይሁን ግራ አካላታቸው የተስተካከለ ይሁን ጆሮአቸው በትክክል መስማት የሚችሉ ሁነው ለክህነት ይመረጡ

29. (ለ) እመሰ ቦ ዘአበየ ቃልከ ይኩን ቅውመ ወሕሩመ እምቤተ ክርስቲያን ወኢታርጉ አንቀፀ መንግሥተ ሰማያት እስመ አንተ መራኁት ዘመንግሥተ ሰማያት ውስተ እዴከ አነ ኵሎሙ ወአንተ ኵሎሙ ዘሃይማኖት ዘዲቤከ።

30. እስመኬፋ ብሂል በነገረዕብራውያን ኰኵሕ ብሂል ወላእሌከ ሐነፅክዋ ለቤተክርስቲያን ወዓናቅፀሲኦል ኢይሄይልዋ ዘነሣእኩ እምኀበአቡየ ወሀብኩከ ወፀገውኩከ መንፈሰ ፀጋየ።

31. ወአንተኒ ከመተሀብ ወትፀጉ ለእለ እምድሕሬከ እለፈተንከ ልቦሙ ወኢይትረከብ ነውር በላእሌሆሙ ዘዕቁብ በቃሉ ዘኢይነብብ ሐሰተ ዘኢያበዝሕ ኪነ ወተግባረ ዝንቱ ዓለም ኃላፊ ዘኢያስቆቁ ሰብእ በሐይደንዋይ።

32. ዘያነሐሲ አበሳ ለጊጉያን ወይመይጦሙ በቃለሰላም ወይትዌከፍ ንስሐሆሙ ለሐጥአን ወይገብር ፍትሐ ዘእንበለአድልዎ ወኢ ነሢአገፅ ወኢ ነሲአ ሕልያን ዘእንበለነሢአሔፕ በሠናይ ህግ ወበርቱዕ ፍትሕ።

33. ዘከመዝኬ ይደሉ ዘትሠይሞ ሊቀካህናት ዘምኩር በኩሉ

በማንኛውም ነገር የሚነቀፉም አይሁኑ።

29. (ለ) ያንተን ቃል አልቀበልም የሚል ካለም ከቤተ ክርስቲያን እንዲከለከልና እንዲርቅ አድርግ ለሱም የመንግሥተሰማያትን በር አትክፈትለት አንተ የመንግሥተ ሰማያት ቁልፍ ነህና በሌላ አባባል የመንግሥተ ሰማያት ቁልፍ ባንተ እጅ ነው እኔ አለት ነኝ አንተም የኃይማኖት አለት መሆንህን አትዘንጋ ሁሉም በእጅህ ነውና።

30. ኬፋ ማለት በእብራውያን ቋንቋ አለት ማለት ነው ቤተክርስቲያንን ባንተ ላይ ሠርቻታለሁ የተጠሉና የረከሱ የሲኦል በሮች አይበረቱባትም እኔ ከሰማያዊው አባቴ የተቀበልኩትን የጸጋየን መንፈስ እነሆ ላንተ ሠጠሁህ።

31. አንተም ካንተ በኋላ ለሚነሱ ንብረትን በመቀማት ሰውን ለሰቆቃ የማይዳርጉትን የዚህን ሐላፊ ዓለም ድሎትንና ከንቱነትን ተረድተው በልሕነታቸው ለሥጋዊ ጥበብ ብቻ ያላስገዙትና በቃላቸው የሚፀኑት ይህንን ታስተላፋለህ።

32. ካንተ በኋላ የሚተካው የበደለኞች ጥፋት ይቅር የሚል ከጥፋታቸው በሰላማዊ አነጋገር የሚመልሳቸው ንሥሐቸውንም የሚቀበል ያለአድልዎ ፍትሕን የሚቀበል ፊቱንም የማይቋጥር ጉቦን የማይቀበል ዋጋ ሳይከፍል የሰውን ንብረት ለመውሰድ የማይመኝ ትክክለኛ ሰው ይሁን።

33. ካንተ በኋላ የቤተክርስቲያን ሊቀካህናት ሊሆን የሚገባው

ምግባረሠናይ እንዘኢያነትግ ትእዛዛተ እግዚአብሔር ዘሰዓታተ ሌሊት ወመዓልት እንዘኢይረሥዕ ዘክሮነዳያን ወሙቁሐን ወግዱፋን ወእለደዴ ቤተክርስቲያን።

34. (ሀ) ወኢይገዝርው ንዋየቤተክርስቲያን ወኢየሀቡ ለሰብአቤቶሙ ወኢለግዩራን አንገማዲሁ ኢያድልው ለገፀሰብእ ኢ ለዓቢይ ወኢለንኡስ ወኢለገፀባዕል ወኢለ ነዳይ።

34. (ለ) ወዘተአዓደወ እምዝንቱ ቃል ሕሩም ወቅውም ውእቱ እምቤተክርስቲያን ወኢይትሐነፅ መልእልቴየ ወመልእልቴክ እለመነኑ ወገደፉ ዘኮነ ዕቁበ ዝንቱ ቃል።

35. ኦ እግዚእየ ከመእዕቀብ ኩሎ ዘአዘዝከኒ ይኩን ፈቃደዚአከ አነሂ እሠርጎ ለቤተክርስቲያን ወለኩሉ ንዋየ ማሕበር ወለኩሉ ንዋየ ምግባሪሃ ወለምሥዋኢሃ ወለመራናታ ወለአረቲሃ ወለጠረጴዛቲሃ ለዲያቆናት ወለመዘምራን ለአናጉንስጢስ ወሕዝባውያን ለእድ ወአንስት ለደቂቅ ወለሕፃናት።

36. በከመአንተ ላእለኵላ አግአዚት ኢየሩሳሌም እንተ በሰማያት ቅድስት ብከ ህግ ዘበበ መዓርጊሁ ለሄራን ሥርዓት ቅድስት ወለእኩያንሰ ቁመት ወግዘት።

በማንኛውም ምግባረሠናይ ተፈትኖ የፀና፣ በቀንም ሆነ በሌሊት የእግዚአብሔርን ትእዛዝ የሚፈፅም ነዳያንንና እሥረኞችን በመንፈሳዊም ሆነ በሥጋዊ መግቦትን የማይረሳ በዓጸደ ቤተክርስቱያን የወደቁትን የሚያስታውስ መሆን አለበት።

34. (ሀ) የቤተክርስቲያንን ንብረት አይበትኑ ለቤተሰቦቻቸውንም አይሥጡ እንዲሁም ለሥጋ ዘመዶቻቸው አያካፍሉ የሰውን ፊት በማየት አያዳሉ ድሐ ሀብታም ትልቅ፣ ትንሽ በማለት ምዕመናን በሚመግቡበት ጊዜ አይበሉ።

34. (ለ) ከዚህ ቃል ወጥቶ የተገኘ ሁሉ የተከለከለ ነው ከቤተክርስቲያንም ይውጣ ባንተ ላይና በኔ ላይም ቦታ አይኖረውም ዋዛ ፈዛዛ ተናጋሪዎች የሚናገሩት ቃል በኔም ሆነ ባንተ ተቀባይነት አይኖረውም።

35. ጴጥሮስ እንዲህ አለ ጌታዬ ሆይ ያዘዝከኝን ሁሉ እፈጽም ዘንድ ፈቃድህ ይሁን እኔ በማሕበር ገንዘብ ሁሉ በቤተክርስቲያን የተለያዩ ንዋያተ ቅድሳት በአገልግሎት ላይ በሚውሉ ንዋያት ሁሉ በጠረጴዛም ይሁን በመሳሰለው እደክማለሁ። በዲያቆናት፣ በመዘምራን በአንባቢያን በሕዝባውያን፣ በሴቶቹም በወንዶቹም አመራሬን አከናውናለሁ።" ለሕፃናትና ለልጆችም እጠነቀቃለሁ።

36. አንተ በሰማያዊቷ ኢየሩሳሌም ቅድስት ለደጋግና በየደረጃው ሥጦታ እንደምትሠጥ ለክፉዎች ደግሞ መለየትን ትሠጣለሁ።

37. በከመሐናንያ ቀሰጠ እምሤጠ ፍሬወይኑ ወአምፅአ መንፈቀ ሤጡ እንዘይፈቅድ በረከተፀጋ ዘመንፈስቅዱስ እስመዓብደ ልቡ ወመሰሎ ዘበወርቅ ይሳየጦ ለፀጋ እግዚአብሔር ዘይቀውም ቅድሜየ አቃቤ ቤተ ክርስቲያን አሕጐለ ነፍሶ ወአውረድዎ ውስተ ሲኦል ታሕቲት ወቀበርዎ ወራዙት።

38. ወአነ ተማዕኩ ላዕሌሁ ወሶበርእየ መልአከ እግዚአብሔር ዘይቀውም ቅድሜየ ዐቃቤ ዘቤተክርስቲያን አሕጐለ ነፍሶ።

39. ወካዕበ መፅአት ብእሲቱ ወሶበሰምዓት ከመሞተ ወድቀት ታሕተ እገርየ ወአስተብቁአተኒ ወእቤላ ለምንት አማዕክምዎ ለመንፈስቅዱስ ኪያሃኒ አሕጐላ ነፍሳ መልአከ እግዚአብሔር።

40. ወልድየ ቀሌሚንጦስ ኢትመሐክ ትትመዐዕ ወትገሥፆሙ ለእለ ተአደውዋ ለቤተክርስቲን እከመ አኮ አንተ ዘትትቤቀል ላቲ ዘአቀመላቲ መልአክ በነገረ ዚአከ ይትቤቀል ላቲ።

41. ውእቱሰ ይገብር በከመ ፈቀደ ወአንተ ቀዲመከ ገሥጽ እንከ ወአስኒ ምግባረከ

42. ወእምዝ ገሥፆሙ ወኢትሕፈሮሙ፤ ዘእንበለ ፍርሐት

37. የሚለዩትም የሐናኒያን መንገድ የተከተሉ ናቸው ሐናንያ ወይኑን ከፍሎ እየሸጠ ያጠራቀመውን ገንዘብ ግማሹን አመጣ በገንዘብም የመንፈስ ቅዱስን በረከትና ፀጋ ፈላጊ አበዳሪና የእግዚአብሔርን ፀጋ በገንዘብ ለመግዛት የሚችል መሰለው በዚሁም ከፊቴ ቆመ ቤተክርስቲያን ጠባቂነትንም ተመኘ በዚህም ነፍሱን አጠፋ ወደሲኦልም ወረደ ጎልማሶችም ቀበሩት

38. እኔም በሱ ላይ ተቆጣሁ የቤተክርስቲያን ጠባቂ የሆነው መልአክ የሱን ሁናቴ ሲመለከት ሐናንያ ነፍሱን እንዳጠፋ ባየጊዜ የሱን ነፍስ አጠፋ

39. በመቀጠል የሐናንያ ሚስት ወደኔ መጣች ባልዋ ሐናንያም እንደሞተ ሰማች ከእግሬ ሥር ወድቃም ለመነችኝ እኔም ለምን አንቺና ባልሽ መንፈስቅዱስን አስቆጣችሁት አንቺም ከሱ ጋር ጠፍተሻል አልኳት ነፍሷንም መልአከእግዚአብሔር እንድትጠፋ አደረገ ይህን ያደረገውም ከእግዚአብሔር ስለታዘዘ ነው።

40. ልጄ ቀሌሚንጦስ ሆይ ቤተክርስቲያንን በሚደፍሩ ሰዎች ላይ ቸልተኝነትን አታሳይ ገሥፃቸው የምትበቀላቸውም አንተ አይደለህም ባንተ አማካይነት የእግዚአብሔር መልአክ ለቤተክርስቲያን ይበቀልላታል።

41. እግዚአብሔር የፈቀደውን ይፈፅማል አንተ ግን ቀድመህ ራስህን ገሥፅ ምግባርህንም አስተካክል

42. ከዚህም አያይዘህ ያለፍርሐት ገሥፅ ስለእውነት እስከደምጠብታ

ተበአስ ዘበእንተ ጽድቅ እበከ ለደም እስመአበደምስ ለሊሁ መልአከ እግዚአብሔር ይቀውም ለቤተክርስቲን እንተአጥረያ በደሙ ወዓተባ በፊፀመስቀሉ።
43. ቀዲሙኑ አርአዮ ወተናገሮ ለሙሴ ከመይገብር ግብራ ለደብተራ እንተ በሰማያት ወአስተጠናቀቀ ሎቱ ነገሮ ዘከመ ይገብር ግብራ ወይቤሎ ሥራዕ ላቲ ከመ ይኩኑ መስተገብራነ ሌዋውያነ እንተባሕቲቶሙ ሥራዕ ሎሙ ሕገ ለደብተራ።
44. ወሰበ ስሕቱ ሌዋውያን ከመካልአን ደቂቀ፳አል ወሰገዱ ለግልፎ ወተምዓ እግዚአብሔር ላእሌሆሙ ወፈቀደ ያጥፍአሙ በምዕር ወአስተርአየ ሙሴ ወወረደ ኀቤሆሙ ወይቤሎሙ ይንሣእ፩ለ፩ ሰይፎ ወይቅትል ቅሩበ።

45. ወበእንተዝ ከመዝ አዘዞሙ በእንተ ዘአርኮሱ ሥርዓታ ለቅድስት ደብተራ እንተወሀቦ በምድር ከመይግበር ኪያየ ደብተራ እንተቦቱ ሐደረ ምስለ ሰብእ እስመፀሐፈ ውስቴታ፲ ቃለተ ጽድቅ በእደዊሁ ቅዱሳት ቀዳሚኩሉ አፍቅሮ ለእግዚአብሔር አምላክከ በኩሉ ልበከ ወበኩሉ ሐይልከ ወበኩሉ ሕሊናከ።
46. አፍቅር ቢፀከ ከመ ነፍስከ ወአክብር ሰንበቶ ለእግዚአብሔር አምላክከ ኢትቅትል ነፍሰ ኢትሑር ብእሲተ ብእሲ

ድረስ ተጣላ የደም ባለቤትስ ከእግዚአብሔር የተላከው ወልድ ነው እሱ በዕፀመስቀሉ ለባረካትና በደሙ ለዋጃት ቤተክርስቲያን ይቆማል።
43. ቀድሞውም ለሙሴ የድንኳንን ሥራ ይሠራ ዘንድ አሳየው ድንኳንዋ ሰማያዊት ናት እግዚአብሔር ስለዚችው ያለውን ለሙሴ ገልያ አጠናቀቀ ድንኳንዋን ሌዋውያን እንዴት ሊያገለግሉዋት እንደሚችሉም ሙሴ ህግ እንዲሠራላቸው ከእግዚአብሔር መመሪያ ተሠጠው።
44. ሌዋውያን እንደሌሎቹ የእስራኤል ልጆች ባጠፉ ጊዜና ለጣዖትም በሰገዱ ጊዜ እግዚአብሔር ባንድ ጊዜ ሊያጠፋቸው ወደደ በዚህ ጊዜ ሙሴ ወደነሱ ወረደና ሁላችሁም ሠይፋችሁን አንሱና ባለሠይፍ የሆነው ሁሉ አጠገቡ ያለውን በያዘው ሠይፍ ይምታው ብሎ አዘዘ።
45. ስለዚህ የድንኳን ሥርዓት ስላረከሱ እንደዚህ አዘዛቸው እቺን ድንኳን ራሱ እግዚአብሔር ከሰዎች ጋር እንዲገናኝባት አድርጎ ይሠራት ዘንድ አስቀድሞ ለሙሴ አዘዘው በሷ ላይም ተጨማሪ አሥር ትእዛዛት ሰጠው የመጀመሪያዋ ትእዛዝ እግዚአብሔር አምላክህን በሀሊናህ ሁሉ በኃይልህ ሁሉና በልቦናህ ሁሉ ውደደው ትላለች።
46. ባልንጀራህን እንደራስህ ውደድ የእግዚአብሔርን ሰንበት አክብር አትግደል አትሥረቅ ከወንድ ሚስት አትሂድ በሐሰት አትመስክር

ኢትሥርቅ ኢትኩን ስምዓ በሐሰት ኢትምሐል በስመ እግዚአብሔር አምላክከ በሐሰት ኢትዘሙ ኢትፍቱ ንዋየካልእ ዘአጥረየ አጥርዮ ወባ – አጓንሂ ብዙሐት ትእዛዛት ዘይመስሉ ለዝንቱ።

47. ወለእለተአደው እምኔሃ ተአዘዘ በህገ ሙሴ ከመይሙት ወይትወገር በአእባን ወበእንተ ሰንበትሂ ለዘአሐዝዎ እንዘይሄልድ ዕፀ በእለተ ሰንበት ወአብፁህዎ ኀበሙሴ ወወሰድዎ ኀበ ወዓልት እስከይስእል ኀበ እግዚአብሔር ከመይሥረይሎቱ።

48. ወነበቦ እግዚአብሔር ለሙሴ ወይቤሎ ቀዲሙ ዘርእዮ ይኩን ሪምዐ ላእሌሁ እዳዊሁ ለሰማዕት ይቅድሙ ወጊረ በአእባን ወእምዝ ኩሎሙ እደው ይውግርዎ በአእባን።

49. ርኢከኑ ለክብረ ደብተራሁ ዘገብረ አንተ ዕቀብ ግብረ ቅድስት ዘይትገበር በውስተ ቅድስተቅዱሳን ጳውሎስኒ ነገሮሙ ለሰብአ ቆሮንቶስ እንዘ ይብል እመቦ ዘስሕተ በቤተክርስቲያን ከመ ኢያስሕት ሕዝበ ክደርስቲያን ሠርውዎ።

50. ወዘንተ ዕቀብ መልእክተከ ከመትንግሮሙ ለእለ ተሰይሙ በመልእክትከ እምድሕሬከ ጳጳሳት ዐእይንተ ቤተክርስቲያን በሎሙ ከመይዕቀቡ ትሩፋተ ከመኢይትመዓዕ

በእግዚአብሔር ስምም በሐሰት አትማል አታመንዝር የራስህ ያልሆነውን የሌላ ሰው ንብረት አትመኝ ሌላ ሰው ያፈራውን ንብረት ለመውሰድ አትመኝ ሌሎችም ይህን የመሰሉ ብዙ ትእዛዛት አዘዘው

47. ይህን የተጻፈውን ትእዛዝ ያፈረሰ ሰው በሙሴ ህግ ይሞት ዘንድ ተወሰነበት ሲሞትም በድንጋይ ተወግሮ ነው ስለሰንበት ደግሞ የተለየ መመሪያ ነበር በእለተሰንበት እንጨት ሲሰብር ሰው ቢገኝ ተይዞ ወደሙሴ ይወሰድ ነበር። ሙሴም ለሌሎች ይሠጠውና ሥርየትን ለማግኘት ይለምን ነበር።

48. እግዚአብሔር ለሙሴ እንዲህ ሲል አናገረው "አስቀድሞ የሌለውን በደል የተመለከተ ሰው ለምስክርነት ይጠራ ጥፋተኛው በድንጋይ ሲደበደብም ያ ምስክር ሰው አስቀድሞ በድንጋይ መውገሩን ይጀምር ከዚያ የቆመው ሁሉ ይውገረው"

49. ስለዚህ ተመልከት ይህን ሁሉ ያደረገው ስለድንኳኑ ክብር ብሎ ነው አንተም በቅድስተ ቅዱሳን ውስጥ የሚፈፀመውን ቅዱስ ሥራ ጠብቅ ጳውሎስም ለቆሮንጦስ ሰዎች በክርስቲያን መካከል ስህተትን የሚከተል ካለ እንዲወገድ አድርጉ አለ።

50. ይህንን በመልእክትህ ላይ ጠብቅ ካንተ በኋላ ለሚሾሙ የእግዚአብሔር ዓይኖች ጳጳሳትም በመልእክት አስተላልፍ ይህን ትእዛዝ በንውሕ ልቦና እንዲጠብቁትና እንዲያስተላልፉት

እግዚአብሔር ላእሌሆሙ ወላእለመርዔቶሙ።

51. ወኢትመጽእ ቃለከ አገዘዞሙ ለእለይሬዕዩ ዎሙ ለመርዔቱ ለክርስቶስ ከመላዕሌሆሙ ይስምዑ ወያፍርሕዎሙ ለእለተሠይሙ ካህናተ ወሊቃነካህናቲሁ ለእግዚአ ሰማያት ወምድር

52. ዘስሙ ጥዑም ለአፍ ዘይትመነዩ ይርዩዎ ወየሐውፅዎ መላእክት ዘሥልጣኑ ዲበኩሉ ነገሥት ወመኳንንት ወላእለ ኩሉ ሐይል እስመ እግዚአ ኩሉ ውእቱ ወአልቦ አድልዎ በኀቤሁ ዘአብርሆ ለፀሐይ ውስተ ጠፈረ ሰማይ።

53. ወአብርሆ ለዓለም በምዕር ወፀሐይኒ ይገብእ ውስቱ ምዕራቢሁ ወያስተጋብእ ብርሃና ለዓለም ወእግዚእነኒ አመ የዐርግ ውስተሰማይ አስተጋብአነ ውስቴቱ ወመሐረነ ከመንግበር ግብራ ለቅድስት ቤተክርስቲያን ወአለበወነ ወአጥበበነ ከመ ንምሐሮሙ ለእለእምድሕሬነ ከመ ይፅንዑ በሥርዓታ ወበሕጋገቲሃ ለቅድስት ደብተራ።

54. ወይቤለነ እግዚእነ ተአምኑ ከመአነ ምስሌክሙ ነበርኩ አንትሙኒ ምስሌየ በከመ ነበርኩ አነ በአቡየ ወበዘፈነወኒ ሊተ አቡየ አነሂ እፌንወክሙ ከመ ትዕቀቡ ሕገ

እግዚአብሔር በነሱ ላይና በመንጋዎቻቸው እንዳይቆጣ ያደርጉ ዘንድ አዘዛቸው።

51. መንጋዎችን ለመጠበቅ የተሾሙትን ካህናት ያስጠንቅቁዋቸው ዘንድና ካህንነትና ሊቀካህናትነት ለሚሾሙ ይመኑዋቸው ዘንድ ጥብዓትን ስጣቸው የነሱ ክህነት በሰማይና በምድር ኃላፊነትን ያስከትላልና።

52. የጌታ ቃል ለአፍ የሚጣፍጥ የሚጥም ነው። ይህን ጥዑም ቃል መላእክት ሰምተው ሥልጣኑ በእጁ የሆነውንና በነገሥታትና በመኳንንት የበላይ የሆነውን የሐይል ሁሉም ኃይል የሆነውን አምላክ ሊያዩት ይወዳሉ በሱ ዘንድ አድልዎ የለም ፀሐይም በሰማይ ጠፈር ያበራ ዘንድ ያደረገ እሱ ነው።

53. ጌታችን ዓለምን አበራው ፀሐይንም ወደመግቢያው ያስገባዋል የሱንም ብርሃን ለዓለም ያደርሳል ጌታችን ባረገ ጊዜ (ወደሰማያት) ወደሱ ሰበሰበንና የቅድስት ቤተክርስቲያንን ሥዕል እንድንሠራ አስተማረን አስተዋይነትን ሠጠን ብልሕነትንም አሳደረብን ይህንን ያደረገበት ምክንያት በኋላችን ለሚነሱ የኛ ተከታዮች በቅድስት ደብተራ ሥርዓትን ይጠብቁ ዘንድ እናስተምራቸው ዘንድ ነው።

54. ጌታችን "እኔ ከናንተ ጋር እንደነበርኩ ታውቃላችሁ እናንተም ከኔጋር እንደነበራችሁ ታውቃላችሁ እኔ ካባቴ ጋር እንደነበርኩና እሱም እንደላከኝ እኔም እናንተን እልካችሁአለሁ የምልካችሁም

ለቤተክርስቲን ከመእሰባሕ በላዕሌሃ።

55. አስመበእንቲአሃ ተሰቀልኩ ወሞትኩ ዕቀቡ ሥርዓተ በፍድፋዴ መእሴባሕ በውስቴታ ምስለ አቡየ ወመንፈስቅዱስ እስመ ኩሉ በሥላሴ ይትገበር ወዓለምኒ ወኵሎን ዘውስቴታ በሥላሴ ተገብረ።

56. ወሶበሂ ታጠምቅዎሙ ለአሕዛብ በሉ በስመአብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ ከመ በ፩ስም ያመልኩሥሉስ አብ ወልድ ወመንፈስ ቅዱስ ወአነሂ እምከመ ተለዓልኩ ወዓረጉ ኀበአቡየ አፌኑ ለክሙ መንፈስቅዱስ ዘኢየኀድገክሙ እጓለማውታ ትኩኑ።

57. ወያዜክረክሙ ኩሎ ዘነገርኩክሙ አቡየኒ ያፈቅረክሙ ፈድፋደ አነ ዘእስእሎ ለአቡክሙ ቀዳሚ በእንቲአክሙ አላ አቡየ ያፈቅረክሙ ወይሰምዓክሙ ወይገብር ለክሙ ኩሎ ዘሰዓልእክምዎ ወአንስ ኢኮንኩ ርኁቀ እምኔክሙ ወእምቤተ ክርስቲያን ወካዕበ እሄሉ ምስሌክሙ ምስለ እለ ከማክሙ እስከ ሕልቀተዓለም።

58. አሌብወክሙ ወአፅንዓክሙ ወመልአክየሂ ይቀውም ለቤተክርስቲያን ይገብር ሎሙ ኩሎ ዘፈቀዱ አንተሰ ንገሮሙ ለስዩማነ ቤትየ ከመይጠናቀቁ እምእኩያን

እኔ የምመሰገንባትን ቤተክርስቲያን ህግንና ሥርዓትን ትጠብቁ ዘንድ ነው" አለን።

55. እኔ ስለቤተክርስቲያን ተሰቀልኩ ሞትኩም በጥንቃቄ የቤተክርስቲያንን ሥርዓት ጠብቁ እኔ አባቴ ጋርና ከመንፈስቅዱስ ጋር በሷ እመሰገን ዘንድ ዓለም ሁሉ በስላሴ ነው የተፈጠረውና ዓለምና በዓለም ውስጥ ያለው ሁሉ በሥላሴ ተፈጥረዋል።

56. በዛን ጊዜ አህዛብን በስመአበ ወወልድ ወመንፈስቅዱስ ስም በሉ ባንድ ስምም ሦስት አካላት እንዳሉ ያምኑ ዘንድ አስተምሩዋቸው እኔም ከምድር ወደሰማይ ከፍከፍ ባልኩ ጊዜና ወዳባቴ ባረግኩ ጊዜ እንደሙት ልጆች የተጣላችሁ እንዳትሆኑ መንፈስቅዱስን እልክላችሁአለሁ።

57. ከናንተ መካከል ሆኜ ያስተማርኩዋችሁን ሁሉ መንፈስቅዱስ እንድታስታውሱ ያደርጋቹኋል አባቴም ይወዳቹኋል እኔ እንደቀድመው ስለናንተ አብን አልለምነውም ነገርግን አባቴ ይወዳቹኋል የምትለምኑትንም ይሠጣችኋል እኔም ከናንተ አልርቅም ከቤተክርስቲያንም አልርቅም ደግሞም እስከዓለም መጨረሻ ድረስ ከናንተ ጋር እሆናለሁ አልለያችሁም።

58. አስተዋዮች እንድትሆኑና እንድትፀኑ አደርጋችሁአለሁ የኔም መልአክ ለቤተክርስቲያን እንዲቆም አደርግላቸው ዘንድ አንተም ለቤቴ ሹማምንት ንሥሐን ሳይፈልጉ ለተንኮል ወደነሱ ከሚመጡ

አሕዛብ እለይመፅኡ ኀቤሆሙ እንዘኢይፈቅድዎ ለንሥሐ ወአዲ አኮ በእንተ አሕዛብ እኩያን ባሕቲቶሙ። ወኢ እምነቢያተ ሐሰትሂ ተዓቀቡ እምእለ ይመፅኡ ኀቤክሙ በአልባሰአባግዕ።

59. ወእንተውስጦሙ ተኩላት ወመሠጥ እለይሜንንዎ ለቃለ እግዚአብሔር ይፌክርዎ ለግእዞሙ ወይሔስው ቦቱ እስመሠይጣን አስሐቶሙ በነገሮሙ ይዌልጥዎ ሎሙ ኀበ ግብሮሙ።

60. አንትሙሰ በሃ ኢትበልዎሙ ወፍኖቶሙ ኢትትልው ለእለይት መሐሉ ምስለ ዲያብሎስ ወይገብሩ ሰገለ ወመቅሰመእሉ ዓላውያን።

61. ረሐቁ እምኔሆሙ ወአዲ ኢታእምሩ ፍናዊሆሙ ወኢትትፋቀሩ ምስሌሆሙ እስመ እመንቱ ውሉደጽልመት ወአንትሙ ውሉደብርሃን ደቂቃ ለቤተክርስቲን እንተ አጥረይክዋ በደምየ ይቤእግዚአብሔር ዘኩሎ ይመልክ

62. ወእፀሐይያ ለማሕቶቶሙ ለእኩያንሕግ እምእድ ወአንስት እምእለ ይትሜሰሉ በኵሉ ተጠይሮ ኢይባኡ ውስተ ቤተክርስደቲያን ዘእግዚአ ሰማያት ወምድር ዘይሴሲ ለኵሉ ያጠቡ እም፬ጠባይዓት ፪ በዘይትገሰስ ወ፪ በዘኢይትገሠሥ። ፫በዘይት ረአይ ወ፩በዘኢይትሬአይ።

ክፉዎች አህዛብ እንዲጠነቀቁ ነገራቸው ድጋሚም ስለእኩያን አህዛብ ብቻ አይደለም በግ ለመድ ለብሰው ከናንተ በኋላ ከሚመጡ የሐሰት ነቢያትም እንዲጠበቁ ነገራቸው።

59. ውስጣቸው ግን የሚነጥቁ ተኩላዎች ናቸው ቃለእግዚአብሔርን ይንቃሉ በተሳሳተ መንገድና ለነሱ እንደሚያመች በማድረግም ይተረጉሙታል በቃለ እግዚአብሔርም ላይ ይዋሻሉ። ሠይጣን አስቶአቸዋልና በማስመሰልም ወደጥፋት ይወስዳቸዋል።

60. እናንተ ግን ሰላም አትበሉዋቸው በነሱ መንገድም አትጓዙ እነሱ ዲያብሎስን ይመስሉታልና የጥንቆላንም ሥራ ይሠራሉና ውስጣቸው በክህደት የተሞላ ነው።

61. ከነሱ ራቁ የነሱን ተንኮል መንገድ አታውቁምና እነሱና እናንተ አንድ አይደላችሁም እነሱ የጨለማልጆች ናቸው እናንተ ደግሞ የብርሃን ልጆች ናችሁ "እናንተ በደሜ ገንዘብ ያደረግሁዋት ቤተክርስቲያን ልጆች ናችሁ" ሁሉን የሚገዛ እግዚአብሔር ይላል።

62. መብራታቸውን አጠፋለሁ እነሱ የህግ ክፍያዎች ናቸውና በዚሁ ክፉሥራ ሴቶችና ወንዶች ይጠመዳሉ በዚሁ ክፋት ተጠምደው ጠንቋዮች ይሆናሉ እነሱ ወደቤተክርስቲያን አይግቡ እሷ የሰማይና የምድርጌታ ማደርያ ናትና። **ሰማያዊው ንጉስ በአራቱ** ጠባይአት ሰውን ይመግባል ሁለቱ የሚዳሰሱ ሁለቱ **የማይዳሰሱ**

63. ወበዝንቱ ጠባይዕ ይሴሲ ለኲሉ ዘነፍስ ወሥጋ ወየዓቁሮ ለማይ በደመና ረቂቅ ወይዘርዎ ለጊሜ ከመሐመድ ወያወርዶ ለበረድ ከመፍተታት ወይለጉሞ ለአንበሪ ወየአሥሮ ለፈያታዊ ይፈትሐ ለትሑት ወያሌዕሎ ለነዳይ እምድር ወያነሥአ እመሬት ለምስኪን።

64. ያስተፈሥሐ ለእመ ውሉድ ወያስተዴሉ ክረምደተ ለምድር በሥርዓታ ለቤተክርስቲያን ቀዳሚ በነቢያት ወዳግመ በሐዋርያት ወእምዝ ወሀበ ሲሲቃውንት ወሉዳ ለጳጳሳት ወለካህናት ወለዲያቆናት።

65. ወካዕበ ለካህናት ወለዲያቆናት ወበመትልው ለመዘምራን ወለአናጉንስጢስ እድ ወአንስት ቤተክርስትያን እንቲአነ ፍሬሃ ከመበቀልት እንዘ አሐተ ለሊሃ ወብዙኃት ሕንባባቲሃ

66. ወአዲ ከመቅርፍተ ሮማን እንዘአሐቲ ፍሬሃ በውስቴታ ከመብዙህ ኅንባባቲሃ ወአካላቲሃ ትኩን ኅብረታ በአሐቲ ስፍነት ወአልቦ ዘይ ከውን በውስቴታ ከመጽምሕው ዘአልቦ ፍሬ ወከመበለስ እንተአልበቲ ፍሬ እንተ ረገማ እግዚእነ።

67. ተአቀብምሙ ከመኢይፅንን ሃይማኖትክሙ አልቦ

ሦስቱ የሚታዩ አንዱ የማይታ ጠባዮች በሰው አሉ።

63. በዚሁ ጠባይእ ሁሉን ይመግባል ነፍስ ያለው ሁሉና ሥጋ ያለው ሁሉ በሱ ይመገባል ውሃን በደመና ይቋጥረዋል ጉምን እንደአመድ ይበትነዋል በረድን በተበታተነ ቅርፅ ያወርደዋል አሣነባሪውን አፉን ይዘጋዋል ቀማኛውን ያሥረዋል በትሕትና ሕይወቱን የሚመራውን ይፈታዋል ነዳዩን ከፍ ያደርገዋል ምስኪኑንም ከመሬት ያነሳዋል።

64. ወላድን ደስ ያሰኛታል ለምድርም ክረምትን ያዘጋጃል ቤተክርስቲያንን አስቀድሞ በነቢያት ከዚያ ቀጥሎ በሐዋርያት መሠረታት ከሐዋርያት ቀጥሎ ደግሞ ለሊቃውንትና ለጳጳሳት በአደራነት አስረከባት።

65. በመቀጠል ለመዘምራን ለካህናትና ለጳድቃን አስረከባት እንዲሁም ለአንባብያን ለወንዶችም ለሴቶችም አስረከባት የቤተክርስቲያን ፍሬ እንደዘንባባ ፍሬ ነው ቤተክርስቲያን አንዲት ስትሆን ብዙ ቅርንጫፎች አሏት።

66. እንዲሁም እነደሮማን ቅራፊ ናት የሮማን ዛፍ ፍሬ እንዴት ሁና (ባንዷ) የሮማን ፍሬ ብዙ ዘሮች አሉ ብዙ አካሎችም አሉ ነገርግን ባንዲት ፍሬ ተጠቃለው ይታያሉ በፍሬዋ ውስጥ እንደጠወለገ ሽት ያለ ፍሬ አይታይም የሮማን ፍሬ ጌታችን እንደረገማት ዕፀበለስም ሆና አትታይም።

67. ከነዚህ መሰሎች ሰዎች ተጠበቁ ሃይማኖታችሁ እንዳይጣመም

ዘይትሜረይ በኮከብ ወኢ በመርፍእ ወኢ በሐፅ ወኢበእክል ወኢበንቃወ አራዊት ወኢተጠያሪ በያፍ ወኢሐላዪ በቃል ለእሉ ኩሎሙ ይረክቦሙ ኩነኔሁ ለእግዚአብሔር፡፡

68. ቦ እለይሠትሩ ገፆሙ በሐፂን ይላፅዩ ጽሕሞሙ አንስትኒ እለይገሥሣ ርኩሰ ወይገብራ ምንሳዌ ላእለ ሥጋሆን አው በእእባን አው በሐፂን አው በዕፀው እምብዙኀ ኀዘን ወቁጥዓ ዘረከቦን፡፡

፷፱. እሙንቱሰ መሰሉ ዘይትበአሱ ምስለ እግዚአብሔር ወኢተመጠው ዘመፅአ ላእሌሆሙ በአኰቴት ኩሎሙ ይሕድጉ ዘትካት ልማደ እመሰ አበዩ ተኰንኖ ይኩኑ ውፁአነ ወስዱዳነ እመቤተ ክርስቲያን

70. ወእመቦ ዘይምህር ደቀ ዘፈነ ወተውኔተ ወአዲ ዘያረውፅ አፍራሰ ወመዓስበ ዓርዌምድር ወፈካሬሕልም ወዘይትዋነዩ፣ እሉ ኩሎሙ ይኅድጉ ዘትካት ልማደ ምግባሮሙ ወለእለሰ ተመይጡ ይኅድግዎሙ ወእመሰ አበዩ ይኩኑ ቅውማነ እምቤተክርስቲን ወእመቦ ዘያፈቅር ሥራየ ወያመልክ ፀሐየ፡፡

ተጠንቀቁ ሃማኖት አለን እያሉ በኮከብ በመርፌ ወይም በጦር በእህል በድንጋይ በአውሬድምፅ በወፍ በዘፈን እና በሌሎችም የሚያመልኩ ሁሉ እናንተን እንዳያሳስቷችሁ ተጠንቀቁ፡፡

68. ሰዎች (ወንዶችም ሆኑ ሴቶች) ሐዘንም ይሁን ሌላ የሚያበሳጭ ነገር ሲገጥማቸው ፊታቸውን በብረት የሚተረትሩ ጢማቸውን የሚላጩ ሴቶች ሁነው በአካላቸው ላይ ጥፋት የሚፈፅሙ በድንጋይ ወይም በእንጨት በሰውነታቸው ላይ ጉዳት የሚያደርሱ አሉ፡፡

69. እንዲህ ያሉ ሰዎች ከእግዚአብሔር ጋር የሚጣሉ ይመስላሉ፡፡ የደረሰባቸውንም ፈተና በአኮቴት አይቀበሉትም እንዲህ ያሉ ሰዎች የወረሱትን መጥፎ ባህል እንዲተው ይነገራቸው የሚሠጣቸውን ምክር ለመቀበል ፈቃደኞች ካልሆኑ ግን ከቤተክርስቲያን ይለዩ

70. ልጆችን ዘፈን የሚያስተምር ካለ ፈረስን የሚጋልብ ካለ በመዓስብነት የሚኖር ካለ ሕልምን በመተርጎም የሚኖር ካለ ማደርያው ጨዋታ ብቻ ያደረገ ካለ እነዚህ ሁሉ ወደቤተክርስቲያን ሲመጡ ይህን ሁሉ የቀድሞልማዳቸው መተው አለባቸው የቀድሞው ልማዳቸውን ለመተው ፈቃደኞች የሆኑትን ሁሉ ተቀበሉዋቸው ፀሐይን በማምለክና የሥራይን ሥራ የሚሠራ ግን ይወገድ፡፡

71. ወእመቦ ዘይሰግድ ለወርሕ ወለኩሉ ኀይለ ሰማያት በአድባር ዘይሰግድ ለፍጥረት ሐዲሳ ለእግዚአብሔር ሰጊደ ወዘ ይዘብሕ እንስሳ በውስተአድባር ውፁዕ ውእቱ እም ቤተክርስቲያን።

72. ወእንዘ ይሰምዕ ዘንተ ወነስሐ ወገብአ አናሕስዮ ሎቱ አበሳሁ በእንተ ፍቅረ ሰብእ ብክሙ አእምሮ ተሀብዎሙ ንሥሐ መጠነገብሩ ብእሲትኒ እንተ አውሰበት ፪ ኤ አሐወ ትሰደድ እስመ አስተቃንኣ ወአፅዐላ አቡሆን ወእሞን።

73. እመሂ ብእሲት ወእመሂ ብእሲ እንዘ ያነሐስዩ ለእመሐደጉ ዘኢርቱዓ አውሰቡ ወተመይጡ ወሐደጉ ዘቀዳሚ እከዮሙ ተወከፍዎሙ በንሥሐ ወመዓድዎሙ ኢይባኡ ኀበ ዘከመዝ አውስቦ።

74. ወለደናግል መሐርዎሙ ለእለኢያውሰቡ ከመይዕቀቡ ድንግልናሆሙ ከመብንተዓይን ብእሲኒ ይገሥፅ ወልዶ ወብእሲትኒ ትገሥፅ ወለታ ወኢይስሐቁ በቅድሜሁ ከመኢያ ምዕዎሙ። አላ በከመሠራዕነ ሕገ ጸሐፉ ሎሙ ሰብሳበ እምድሕረ ሐተትክምዎሙ ወፈተው።

75. ወለእለሰ ሐረዩ ከመ ይትዓገሡ አቅምዎሙ ቅድመቤተ

71. ለጨረቃና ለሰማያት ኃይላት ለተራሮችና ለሌሎችም ፍጡራን የሚሰግድና ለእግዚአብሔር መስገዱንም የተወ ቢኖር እንስሳትን እያረደ ለፍጡራን ተራሮች መስዋዕት የሚያቀርብ ሁሉ ከቤተክርስቲያን ይወገድ።

72. የካህናትን ምክር ሰምቶ ንሥሐ ከገባ ያለፈውንም ሥሕተቱ አስታውሶ ከተፀፀተ በፈፀመው ስሕተት መጠን ቅጣቱን ሥጡት ይህንን ለማገናዘብ አእምሮ አላችሁና ሴት ሁለት ወንድማማችን ብታገባ ከቤተክርስቲያን ትባረር ወንድም እንዲሁ ሁለት እታማማቾችን ቢያገባ ይሰደድ ባባትና እናታቸው ላይ ስድብን አመንጭቷልና

73. ወንድም ይሁን ሴት ይህን የመሰለ የተሳሳተ ጋብቻ ትተው ከተመለሱ ደግሞ ይህን የመሰለ ስህተት እንዳይፈፅሙ በመምከር ወደቤተክርስቲያን አስገቡዋቸው። የተስተካከለ ክርስቲያናዊ ጋብቻም እንዲኖራቸው አድርጉ።

74. ለደናግልም የወደፊቱ ጋብቻቸው ይዞታ የተቃና እንዲሆን እስከዚያውም ድንግልናቸውን በጥንቃቄ ይጠብቁ ዘንድ ምክሩዋቸው ድንግልናቸውን እንደዓይን ብሌን ይጠብቁት በዚህመሠረት አባት ልጁን ይገስፅ እናትም ሴት ልጇን ከመምከር አትቦዝን በአመንዝራነት መንገድ ጋብቻ አይፈፀም እኛ በሠጠናችሁ ,ህግ መሠረት ይፈፀም እንጂ።

75. ድንግልናቸውን ጠብቀው ለመኖር የወሰኑትን ሁሉ

እግዚአብሔር ወፈሐርዎሙ ለመርዓዊ ሰማያዊ ከመይዕቀቡ ርእሶሙ ወእመሰ ኢክሂሉ ተዓግሦ ይሕበሩ በህገቀኖና ሰብሳብ በአሐቲ ብእሲት ምስለ ፈሪሃ እግዚአብሔር እስመ ንፁህ ሰብሳብ ቡሩክ በኀበ እግዚአብሔር።

76. ወእግዚአብሔር ፈጠሮ ለአቡነ አዳም በአርአያሁ ወበአምሳሊሁ ወወሀቦ አንተ ብእሲተ ሔዋንሃ ባረኮሙ ወይቤሎሙ ብዝኁ ወተባዝኁ ወምልእዋ ለምድር ወከመዝ አዘዘ እግዚአብሔር ይንበር ክርስቲያናዊ በአሐቲ ብእሲት።

77. ወለእለሰ ይነብሩ ምስለ ብዙሐን አንስት ዘኢተአዘዘ በሕግ ኢይትኄለቁ ምስለ አበግዓ መርዔቱ ለክርስቶስ ወለእመሰ ሰብዓ ነስሐ አናሕስዩ ሎቱ ይክል ተሣለቆ ወለእመ አበየ ይትረገም ይኩን ውጹእ እመቤተክርስቲያን።

78. ወከመዝ ሥርዕዋ ለቤተክደርስቲን ኵሉ ጊዜ ከመይህድር እግዚአብሔር ውስቴታ ወአምሳል ለክሙ አምላኬሁ ለዝንቱ ብእሲ ባዕል ፩ ዘሐነፀ ቤተ ሠናየ ሥርግወ ወብሩሃ ኩለንተሁ ፈድፋደ ወባቲ ፯ አዕማድ

79. ሰብዓቱሰ ድድ ሠናይ ፈድፋደ ወመንሰጉሰ በዘይደሉ ወመፍትሔሁሰ በዘይበቁዕ ወገብረ ውስቴቱ ፯ መማክርተ ወሰብዓስ ሴመ ላእሌሆሙ ዘይኤዝዞሙ ለኵሎሙ ወገብረ

ከእግዚአብሔር ፊት አቁሙአቸው ለሰማያዊው ሙሽራም የታጨ እንዲሆኑ አድርጎ እነሱ ራሳቸውን በድንግልናዊ ሕይወት ለመምራት ይችሉ ዘንድ በዚሁመንገድ ሕይወታቸውን ለመምራት ካልቻሉ ግን በቤተክርስቲያን ህግ መሠረት ይጋቡ ንፅሕናን የተላበሰ ጋብቻ የተባረከነውና።

76. እግዚአብሔር አባታችን አዳምን በአርአያውና በምሳሌው ፈጠረው አንዲት ሚስትንም ሠጠው እሷም ሄዋን ናት እግዚአብሔር ባረካቸው ብዙ ተባዙም አላቸው በዚህ መሠረት እግዚአብሔር የሰው ልጅ በክርስቲያናዊ ሕይወት እንዲኖር አዝዞታል።

77. ከብዙ ሴቶች ጋር ለሚኖሩ ግን ከሕግ የወጡ ናቸውና ከኢየሱስ ክርስቶስ መንጋዎች ጋር አይቆጠሩም ድርጊታቸውን ትተውና ተፀፅተው ከተመለሱ ግን ከምዕመናን ጋር ይቆጠራሉ ከመጥፎድርጊታቸው ካልተመለሱ ግን ከቤተክርስቲያን ይለዩ።

78. ቤተክርስቲያን በዚሁ መንገድ ሥርዓት አስቀመጡላት ሁልጊዜ እግዚአብሔር ያድርባት ዘንድ ለዚሁም ምሳሌ ልስጣችሁ ምሳሌው አንድ ኃብታም ሰው የሠራውቤት ይሆናል አንድ ሰው የምታምር አዳራሽ ሠራ ሰባት ምሰሶዎች ነበሩዋት።

79. ሰባተኛው ምሰሶ ከማሕል ተተክሎ ሁሉንም ተሸክሟል በጣምም ያምራል መቆለፊያውም በሚገባ ተዘጋጅቷል ለዚሁ መልካም አዳራሹ ሰባት አማካሪዎችን አስቀመጠ ሰባተኛው አማካሪ

፪ሰብአ ዓይን እለ ይኔፅሩ ሠናየ ወእኩየ።

80. ወገብረ መትሕቴሆሙ ፪ ፀዋርያነ እለይፀውሩ ኩሎ ወሴመ ፲ ገባረ እምኔሆሙ እለ ይኤዝዞሙ ኀበኩሉ ዘፈቀዱ ከመይግበሩ ሥምረቶ።

81. ወፍካሬሁሰ ለሊሁ እስመይቤ ተዓውቀ እግዚአብሔር በይሁዳ ወዓብየ ስሙ በእሥራኤል ወገብረ ሰላሞ ሐሮ ወማሕደሮስ ውስተ ፅዮን ወበህየ ሰበረ ኃይለ ቀስት ወልታ ወኲናተ ወፀባዒተ

82. ወዝንተ ሠራእከ ከመይፅናዕ መሠረተ ሃይማኖቶሙ ለውሉደ ቤተክርስቲን ከመይሕድር እግዚአብሔር ኀቤሆሙ ወይረስዮሙ ማሕደረ ክቡረ ኀበ ሐነፀ ቤቶ ምስለ አቡሁ ኄር ወመንፈስ ቅዱስ ማሕየዊ።

83. ወካዕበ ንግሮሙ ለሥየማነ ቤተክርስቲን ከመኢይትሀየዩ ንሥሐ ሐጥአን እስመይቤ ለሊሁ እግዚእነ ኢታቅብዱ ፀረ ክቡደ ዲበ አሕዛብ ዘኢይክሉ ፀዊረ አንትሙሰ በዲበ ልቡና አንገሊገክሙ ሥርዐዋ ለቤተክርስቲያን ከመ አዘዝናክሙ በጉባዔነ እንዘ ሀሎነ አሐተኔ።

84. ለሊሁሰ እግዚእነ አዘዘነ በመንፈስቅዱስ ቀዲሙ ኩነ

ሁሉንም ይመራል። ሁለት ሰላዮችንም መደበ እነዚህ ሁለት ሰላዮች መልካሙንና ክፉውን አንድ ባንድ ይቆጣጠራሉ።

80. ከነዚህ ሁለት ሰዎች በታች ሁለት ተሸካሚዎችን መደበ ሁለቱ ማንኛውንም ሁሉ ይሸከማሉ ከዚያ አሥር ሰዎችን ሾመ እነዚህ ሁሉ ወደፈለገው ሁሉ የሚታዘዙ ናቸው ወደፈለገውም ሁሉ ያዛቸዋል።

81. ለዚሁም ትርጓሜው እግዚአብሔር በይሁዳ ታወቀ በእስራኤል ዘንድም ስሙ ከፍ አለ ባገሩም በሰላም ኖረ ማደርያውንም በፅዮን አደረገ በዚህም የጦርን ሐይል ሰበረ ሰልፈኛንና ጋሻንም አጠፋ ማለት ይሆናል።

82. የቤተክርስቲያን ልጆች መሠረት ይፀና ዘንድ አንተ ይህንን ሥርዓት ትሠራለህ መሠረታቸውም ሲፀና እግዚአብሔር በነሱ ላይ ያድራል ካባቱ ጋርና ከመንፈስቅዱስ ጋርም የሱ ማደርያ ያደርጋቸዋል።

83. ደግሞ ሐጢአተኞችን ንሥሐ ችላ እንዳይሉ የቤተክርስቲያንን ሹማምንት ንገራቸው ጌታችን ኢየሱስክርስቶስ በአህዛብ ላይ ሸክምን አታክብዱ የማይችሉትንም ሸክም አታሸክሙአቸው ብሏል እናንተስ ይህንን እንዳትፈፅሙ አስተዋይ አእምሮ አላችሁ። አንድላይ ተሰብስበን በሠጠናችሁ ሥርዓትም ቤተክርስቲያንን ምሩአት

84. ጌታችን ራሱ በመንፈስ አስቀድሞ ልባሞችና አዋቂዎች እንሆን

ማዕምራነ ወለባውያነ በውስተ ውሳጤ መንጠላዕት ወኢይትረከብ በላ እሌክሙ ሕሱም ዘያርሕቀክሙ እምእግዚአብሔር አምላክክሙ።

85. ወእምዝ ካዕበ ተጋብኡ ከመታስንዩዎሙ ለአሕዛብ ወኢይርከብ በላእሌክሙ ነውረ ከመይትፌሣህ እግዚአብሔር በእንቲአክሙ ወበእንቲአሆሙ ከመ ትበሉ አመንቀውም ቅድሜሁ ንሕነ እለገበርነ ዘአዘዝከነ ወመሀርነ ለህዝብከ ከመይግበሩ ከማሁ።

86. እግዚኦ ኢትስድደነ ምስለርጉማን እለተግሕሱ እምትእዛዝከ አላ ጉልቄነ ምስለ አባግዒከ እለዐቀቡ ትእዛዘከ ወኢትረስየነ ግሑሳነ እምሕረትከ ወዘንተ ሶበትብልዎ ይትፌሣህ ብክሙ ምስለደቂቅክሙ ወትወርሱ ምድረ ሐዳሰ ምስለ ኄራን ወፃድቃን።

87. እስመእምኩሉ አሕዛብ ዘሰማዕክሙ ወዘርኢክሙ እምዘብክሙ አበሳ ዘዘኢአሁ ይገብሩ ገሥፅዎሙ ከመኢይውቅስክሙ እግዚአብሔር ወለእመአርታዕክሙ በዘርኢክሙ ወሰማዕክሙ ይከሥት ለክሙ እግዚአብሔር ሕቡአተ ዘኢያእመርክምዎ ቀዲሙ።

88. ወበእንተዝ ትሴኒ ቅድስት ቤተክርስቲያን አንተሙኒ ኖሎት ትትጋበኡ ቃለ በእለተደይን እመሂ ሠናየ ወእመሂ እኩየ ሠናይሰ ለሠናያን ውስተ ማሕደረ ብርሃን ኀበአልቦ ደዌ

ዘንድ አዞናል አስተዋይነታችን ከመጋረጃ ውስጥ ካለው ቅድስና ቦታ ይሆን ዘንድ በናንተ ላይም ክፉ አይገኝ ክፉ ነገር ከእግዚአብሔር እንድትርቁ ያደርጋል።

85. ከዚህም ሌላ እንደገና ተሰብሰቡ አሕዛብን ታሥተምሩአቸው ዘንድ እግዚአብሔር ደስ ይለው ዘንድ በናንተ ላይ ነውር አይገኝ በዚያች ከፊቱ በምንቆምባት እለት አህዛብ ሊሠሩት የሚገባቸውን እንድናስተምራቸው አዘዝናል እኛም ያዘዝከንን አስተምረናቸዋል ብለን ለመመለስ እንችል ዘንድ።

86. አቤቱ ከተረገሙትና ከትእዛዝህ ከራቁ ጋር አትስደደን ትእዛዝህን ከሚጠብቁ መንጋዎችህ ጋር ቁጠረን እንጂ ከምሕረትህም የራቅን አታድርገን ስትሉት አስተምራችሁ በጸጋ ከወላጆቻችሁ ጋር ይደሰትባችኋል። ከፃድቃንና ከደጋግ ሰዎች ጋርም አዲስ ምድርን ትወርሳላችሁ።

87. ከምታስተምሩዋቸው አህዛብ መካከል የሚፈፅሙትን በደል ብታዩ አትለፉዋቸው ገሥፁዋቸው እንጂ ይህን ካላደረጋችሁ እግዚአብሔር ይወቅሳቹኋል ባያችሁትና በሰማችሁት ሁሉ በቅንነት ካስተማራችሁ እግዚአብሔር አስቀድማችሁ ያላያችሁትን የተደበቀ ነገር ይሠጣቹኋል

88. ስለዚህ ቅድስት ቤተክርስቲያን አምራ ትታያለች እናንተም እረኞች በቃል ትሰበስባላችሁ ክፋታችሁና ደግነታችሁ ያንጊዜ ይታያል ደጉ ሕመምና ምንዳቤ ከሌለበት የብርሃን ማደርያ

ወአልቦ ሕማም

89. እኩያኒ ለእኩያን ውስተ ማህደረጽልመት ኀበ ሀሎ ነደ እሳት ወኩነኔ ዘለዓለም ኀበነሎ ሥቃይ ወነቅየ ስነን እንተ አልባቲ ሙዓእ እስከ ለዓለም።

90. ዕቀብዋ ለዛቲ ቃልየ ወለዛቲ ሥርዓትየ ከመ ትትፌስሑ በዓውዱ ለአምላክክሙ ወትከውኑ ሊቃናተ ዲበእለመሐርናክሙ በከመ አስፌወነ እግዚእነ ወይቤለነ አመዳግም ምዕአትየ አመእነብር ዲበ መንበረ መንግሥትየ ትነብሩ ዲበ፲ወ፪ነገደ እሥራኤል።

91. ለእመ አመንክሙ ብነ በቃልነ በሠናይ ሕግ ኩኑ ሠናያነ ወለእለኢአምኑ ብነ በቃልነ ወስብሐቲነ ይትኰነኑ በደይን እስከለዓለም

92. አንትሙኒ ለእመ መሐርክምዎሙ በሠናይ ትከውኑዎሙ ሊቃውንተ ወትትፌስሑ ውስተ ገነተ ትፍሥህት ምስሌሆሙ ወዕለሰ ኢሰምዑክሙ ቃለክሙ ይትኰነኑ አንትሙኒ ለእመኢያሰነይክሙ ምግባሪክሙ ትትኰነኑ በደይን ኀቡረ።

93. አንትሙኒ ኢያሰነይክሙ ምዝጋናክሙ እንተፀውዓክሙ ባቲ አነ ቀሌሚንጦስ እነግረክሙ ገሀደ ጥቡዓነ ኩኑ ከመ ትገሥዕምሙ ለሐጥአን ወትሚጥዎሙ ለዕልሕዋን

ይሆናል።

89. ክፉ [illegible] የጥርዕ ማፋጨትና ሥቃይ ካለበት በዚህ ቀን [illegible] ሐዘንና መከራ ልቅሶና ዋይታ ካለበት [illegible] በእሳት እየተቃጠለ ይኖራል።

90. [illegible] እቺንም ሥርዓቱን ጠብቁዋት ይህንን [illegible] አደባባይ ትደሰታላችሁ [illegible] ያንጊዜ አለቆች ትሆናላችሁ ይህንንም [illegible] ምዕአቱ በአሥራ ሁለት [illegible] ተቃምጠን በአሥራሁለቱ ነገደእሥራኤል ላይ [illegible] እንደምንችል ገልፆልናል።

91. [illegible] በመልካምም ህግ ከተመራችሁ መልካም [illegible] ለማያምኑ ግን ምስጋና[illegible] ለማይቀበሉ ዘለዓለማዊ ደይን ይጠብቃቸዋል።

92. እናንተ [illegible] አስተምራችሁ ለመንግሥተሰማያት ካዘጋጃቹኋቸው ለነሱ ዓለቆች ትሆናላችሁ በመንግሥት ለማያትም ከነሱ ጋር ደትደሰታላችሁ ነገርግን በትክክል ሳታስተምሩዋቸው በመቅረታቸው ለኩነኔ ቢዳረጉ እናንተና እነሱ አብራችሁ ገሐነመእሳት ትገባላችሁ።

93. እናንተ ቸልተኞች ከሆናችሁ አካሄዳችሁም ካላሳመራችሁ በእግዚአብሔር የተጠራችሁበትንም ጥሪ ካላከበራችሁ ፍዳ ይጠብቃቹኋል እኔ ቀሌሚንጦስ እነግራችሁአለሁ ጥቡአን ሁኑ

እምእከዮሙ ወአስምዑ በእንተአሆሙ ሰማየ ወምድረ።

94. በከመ ይቤ ነቢይ አፅምዕ ሰማይ ወእንግርከ ወትሥማዕ ምድር ቃለአፉየ ወካዕበ ይቤ በውስቴቱ በዝሙር ዝ ሕዝብ አብድ ወአኮ ጠቢብ አኮኑ ዝንቱ አብ ፈጠረከ ፈጠረከሂ ወገብረከ ወካዕበ ይቤ በውስቴቱ ለዝ መዝሙር በልዓ ያዕቆብ ወፀግበ ሰብሐ ወገዝፈ ወርሕበ ሐደጎ ለእግዚብሔር ፈጣሪሁ ወርሐቀ እምእግዚአብሔር ሕይወቱ።

95. ወከማሁ አንትሙኒ ኖሎት ኅሥፅምሙ ለሕዝብ እለእምታህቴክሙ ወመሐርዎሙ ሥርዓተ ቅድስተ ዘተወፈይክሙ በዕለት ቅድስት

96. ዘተወለድክሙ በዕለት ቅድስት ወዓባይ እንተ ባቲ ዐተቦሙ ንሥኡ ፀጋ መንፈስቅዱስ ላዕሌክሙ አቅድሙ ዓቂበ ሥርዓታ ለዛቲ ሃማኖት ወመሀርዎሙ ለሕዝብ ከመ ይዕቀቡ ኪያሃ።

97. እስመኵሉ ዘያፈቅር ያቅርብ ማዕደ መንፈሳዊተ ወኢይጥዕም እምኔሃ ሐሳዊ ውእቱ

98. ወሶበ ትነግሩ ለሊክሙ ወኢትትዓቀቡ አልቦ ዘይሠጠወክሙ ወካልአን ይብሉ ሶበለሊሆሙ ገብርዎ እምዘነገሩነ

ስለዚህ ሐጢአተኞችን ልትገሥፁዋቸው ትችላላችሁ አታላዮችንም ከተንኮላቸው ልትመልሱዋቸው ትችላላችሁ ስለነሱም የሰማይንና የምድርን ምሥክርነት ጠይቁ።

94. ነቢይ ስለዚህ ሰማይ ስሚ ልንገርሽ ምድርም አድምጪ (የአፌን ቃል ስሚ) እንደገና ከዚሁ መዝሙር በመቀጠል ይህ ሕዝብ ሰነፍ ነው ብልህ አይደለም ይህ አልነበረም የፈጠረህ ፈጥሮም ሕይወትን ሠጠህ እንደገና በዚሁ መዝሙር ቀጥሎ እንዲህ አለ ያዕቆብ በልቶ ጠገበ ሰባ ደነደነም ወድያውም ተራበ እግዚአብሔርንም ፈጣሪው ተወው ሕይወቱም ከእግዚአብሔር ራቀ።

95. እንደዚሁ እናንተም እረኞች ከበታቾቻችሁ ያሉትን ሕዝቦች ገሥፁዋቸው የተቀደሰችውንም ሥርዓት አስተምሩዋቸው።

96. ይህን ሥርዓት የመንፈስቅዱስን ፀጋ ትቀበሉ ዘንድ በታላቋና በተቀደሰቿ ዕለት የተቀበላችሁት ነው ከሁሉ በፊት ከሁሉ አስቀድማችሁ የዚያችን ሃይማኖት ጠብቁ በመቀጠልም ሕዝብ እሷን ይጠብቁ ዘንድ አስተምሩዋቸው።

97. መንፈሳዊ ማዕድን ለማቅረብ የሚወድና ነገርግን ከሷ የማይቀምስ ሁሉ ውሸታም ነው።

98. የምትናገሩትን ለመሥራት ዝግጁዎች ሁኑ ይህ ካልሆነ ግን የምትናገሩትን የሚያዳምጥ የለም ሌሎች የሚናገሩትን ራሳቸው

ኢሰማዕናሆሙ ወእምነገነበር ነቃሎሙ።

99. ይእዜኒ ይሜህሩነ ወኢይገብሩ እፎ ንሰምዖሙ ወንገብር ትእዛዞሙ ንሕነሂ ነሐውር በከመ ገብሩ ለሊሆሙ ሊቃውንተ ቤተክርስቲያን ዕቀቡ ትእዛዘ እግዚአብሔር ወኢታድልው ለገጽ በውስተ ፍትሕ።

100. ወኢትንሥኡ ሕልያነ በላእለ ንፁሕ ዝኒ የአኪ እምኩሉ እስመ የዐውር አዕይንተ ልብ ወያፀልም ጥበበ ኢታድልው ለገፀ ባዕል በብዕሉ ወኢትግሥሡ ፍትሐ እንለማውታ በእንተ ንዴቱ።

101. እስመ እግዚአብሔር አቡሁ ለነዳይ ወረዳኢሁ ለዘአልቦ ረዳኢ ወእመይጥ ገፅየ እምእለይረስዕዎ ለቃልየ ወትእዛዘየ እስከአጠፍኦሙ ወእሜሩ እምድር ዝክሮሙ ለእለይትዔየርዎ ለቃልየ።

102. ወይከውኑ ርእሳ ለቤተክርስቲን እለያፈቅሩ ምሒረ ቃለ ጽድቅ ወያርእይዎሙ ፍኖተየ ለሕዝብ ወያሠረግውዋ ለቤተክደርስቲያን ሠርጐ ሠናየ ዘውእቱ ትምህርትየ።

103. ኤጴስ ቆጶስ ዘያሠርጉ ማእዶ በጣዕመ መባልዕት እንዘርሁባን ሰብአህገሩ ኢኮነ ኤጴስ ቆጶስ ወእንዘዕሩቃን

በሠሩት ኑሮ እኛም በሠራነው ነበር ትምህርታቸውንም በተቀበልነው ነበር ይላሉ።

99. ነገርግን የሚያስተምሩንን ራሳቸው አይሠሩትም እንዴት እንሰማቸዋለን ትዕዛዛቸውንስ እንዴት እንፈፅማለን ይልቁንስ በነሱ አካሄድ እንሄዳለን ይላሉ የቤተክርስቲያን አለቆች ሆይ የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ጠብቁ በፍርድ ጊዜም የሰውን ፊት አይታችሁ አታዳሉ

100. ከንፁሕ ሰው ላይ መማለጃ አትያዙ ይህ ድርጊት ከበደል ሁሉ የከፋ ነው የልቡናን ዓይኖች ያሳውራልና ጥበብንም ያጨልማልና ባለፀጋን በባለፀግነቱ ብቻ የበላይነትን አትሥጡት የሙትልጆችንም ችላ አትበሉ

101. እግዚአብሔር ለነዳይ አባቱ ነው ረዳት የሌለውንም ይረዳዋል። ቃሌን ከሚረሱ ላይ ፊቴን እመልሳለሁ እነሱንም ሥራቸውን ነቅየ ከምድር አጠፋቸዋለሁ በቃሌ ላይ የሚገዳደሩትን እንዳልነበሩ አደርጋቸዋለሁ።

102. የእምነትን ቃል ማስተማር የሚያዘወትሩ ሁሉ የቤተክርስቲያን አለቆች ይሆናሉ። እነዚህ ሕዝባብን የኔን መንገድ ያሳዩአቸዋል የኔን ትምህርት የሆነውን በማስተማር የተመሠረተ መልካም ሽልማትም ቤተክርስቲያንን ያሸበርቁዋታል።

103. ያገሩ ሰዎች በረሐብ ተይዘው እያለ በልብስ እርዛትም ሆነ በውሃ ጥማት እየተቸገሩ እያለ የተለያየ ጣዕም ያላቸውን

ወርኀባን ወፅሙአን ወሕጡአን ሲሳየዕለቶሙ ለውእቱኬ ይትመዓፃ እግዚአብሔር እስመ ኢያሰነየ መልእክቶ።

104. ሰብአብሔር እንዘ መንፈቆሙ ይበልዑ ወመንፈቆሙ ይርሕቡ እንዘመንፈቆሙ ይለብሱ መንፈቆሙ የሐውሩ ዕሩቃነ ወይፀንሑ ርኅባን እምሕብስት እንተ አሰፈዎሙ እግዚአብሔር ለኄራን ስዩማነ ቤተክርስቲያን።

105. ውእተ አሚረ ይኔስሑ እለኢአቀቡ ትእዛዘ እግዚአብሔር ወሥርዓታ ለቤተክርስቲያን። ወእለሰ ኢያሰነዩ መልእክቶሙ ለእለከማሆሙ ሎሙኬ ይከልእዎሙ ማዕደ ይጌስዖሙ ወይቤ ሎሙ ረኀቁ እምኔየ ኵልክሙ ገበርተ ዓመፃ።

106. ወይቤሎሙ ኢየአምረክሙ በእንደተ ዘኢገበርክሙ ሠናየ ላእለነዳያን ወምስኪናን አሐዊክሙ ወአነሂ ኢይሁበክሙ ዘአሰፈውኩ ለአበዊክሙ እለይትለአኩ በርትዕ ለቤተክርስያን እንተ አጥረይክዋ በደምየ ይቤ እግዚአብሔር

107. እስመኵሉ ዘአዕበየ ርእሶ የሐሥር ወኵሉ ዘአትሐተ ርዕሶ ይከብር ስማዕ አ ፅሩዕ ዘትሜንን ቢጸከ ወታዐቢ ርእሰከ ኢያእመርከኑ ከመዓርገ ቤተመቅደስ ፈሪሳዊ ወመፀብሐዊ

መባለዕት እያቀያየረ የሚመገብ ኤጴስቆጶስ ኤጴስቆጶስ ተብሎ ሊጠራ አይገባውም ይህ ዓይነቱ ኤጴስቆጶስ ከእግዚአብሔር ዘንድ ፍዳ ይጠብቀዋል ኃላፊነቱን በፍፁም ሊወጣ አልቻለምና።

104. ያገር ሰዎች ግማሻቸው ሲበሉ ምን ጊዜም ከመካከላቸው ጦምአደሮች አሉ። ግማሻቸው ሲለብሱ በልብስ እጦት የሚራቆቱም ይኖራሉ ረኃብተኞች እግዚአብሔርን የሚያምኑ ከሆነ ለቤተክርስቲያን ደጋግ መሪዎች ያዘጋጀውን (እግዚአብሔር) ምግብ ይመገባሉ።

105. የእግዚአብሔርን ትእዛዝና የቤተክርስቲያንን ሥርዓት ያልጠበቁና ተልእኮአቸውንም ያልተወጡ ሁሉ በንዝህላልነታቸው ምክንያት ወልድ በግርማመንግሥቱ ሲመጣ እናንተ የዓመፅ ልጆች ከኔ ራቁ ተብለው ዳግም ሞትን ይሞታሉ።

106. በነዳያንና በምስኪን ወንድሞቻችሁ ላይ መልካም ሥራን ስላልሠራችሁ አላውቃችሁም በደሜ ገንዘብ ያደረግሁዋትን ቤተክርስቲያንን በቅንነት ለሚያገለግሉ ቃል የገባሁላቸውንም በረከት ለናንተ አልሠጥም ይላል እግዚአብሔር።

107. ራሱን ከፍ ያደረገ ይዋረዳል ራሱን ዝቅ ያደረገ ደግሞ ይከብራል አንተ ባልእንጀራህን የምትንቅ ጥፉ ራስህን ከፍ የምታደርግ ፈሪሳዊና መፀብሐዊ ሊፀልዩ ቤተመቅደስ እንደገቡ

ፈሪሳዊሰ ፀለየ በትዕቢተ ልቡ ወአእተተ እግዚአብሔር ጸሎቶ።

108. መወፀብሐዊሰ ኢቦአ ቤተመቅደሰ አላ ፀለየ እማዕምቀልቡ ገዓረ ወበከየ እንዘይብል ኢይደልወኒ አንሥእ አዕይንትየ ውስተ ሰማይ እምብዝኅ ጌጋይየ ወአበሳየ ውእቱሰ ጸድቀ እምዝንቱ።

109. ወካዕበ ኢትሌብውኑ ዘይቤ በወንጌል ምንተ ትቤይን ሐሠረ ዘውስተ ዓይነ ቢዕክ ወኢትሬኢ ሠርዌ ዘውስተ ዓይንክ ከመትብሎ ለእሁክ አውፅእ ኃሠረ ዘውስተ ዓይንክ ወእምዝ አውፅእ ሠርዌ ዘውስተዓይንክ ወእምዝ ትሬኢ ወታቤይን ለአውፅኦ ኀሠረ እምዓይነ ቢጽከ እስመ ከልአ እግዚአብሔር ኢያዕብዩ ርእሶሙ ወኢይመንኑ ቢያሙ።

110. ኢትረስዩ ለክሙ መከራ ከመትመንንዎ ለቢፅክሙ ወኢታዕብዩ ልበክሙ እስመ ነበሀሎ ትዕቢት ህየ ሀሎ ኃሣር ሐሰ ለክሙ ከመኢትግበሩ ሐሣረ ዲበ ላእካነ ዘቤተክርስቲያን እንተ አስነያ እግዚአብሔር በኩሉ ሥርዓት ወናሁ ዘይገብር ላዕሌሃ ዘከመ አዘዝነ ሐቢረነ ወለነኒ አዘዘነ እግዚአብሔር አምላክነ ወመድኅኒነ ዘትፈቅዱ ይግበሩ ለክሙ ሰብእ ከማሁ አንትሙኒ ግበሩ

አታውቅምን ፈሪሳዊው በትዕቢት ሥለጸለየ ጸሎቱን እግዚአብሔር አልተቀበለም

108. መፀብሐዊው ግን ቤተመቅደስ እንኳ ለመግባት አልደፈረም ከሕሊናው በጥልቅ እየተጸጸተ በከባድ ሰቆቃ ተይዞ ወደሰማይ ዓይኖቹን ከፍ በማድረግ ለመጸለይ አይገባኝም በደሌና አበሳየ እጅግ ከመብዛቱ የተነሳ ረክሼአለሁና አለ እንጂ እሱም ከመጸጸቱ የተነሳ ጸደቀ

109. ዳግመኛስ በወንጌል በዓይንህ ምሰሶ እያለ በጓደኛህ ያለውን ጉድፍ ለምን ታያለህ በዓይንህ ያለውን ምሰሶ ለምን አትመለከትም ባልንጀራህን ከዓይንህ ውስጥ ጉድፍ አለና አውጣ ለምን ትለዋለህ አስቀድመህ በዓይንህ ያለውን ምሰሶ አውጣ ከዚያ በኋላ ባልንጀራህን በዓይንህ ጉድፍ አለና አውጣው ትለዋለህ እግዚአብሔር ራስህን ከፍ ማድረግና ባልንጀራህን ዝቅ ማድረግ ከልክሏል።

110. ባልንጀራችሁን ለመናቅ የሚያነሳሳ ነገርን አትፈልጉ ልቡናችሁም በትዕቢት አይሞላ ትዕቢት ካለበት አካሄድ ከዚህ ውርደት አለ አይሆንም በቤተክርስቲያን አገልጋዮች ላይ ውርደትን አታምጡባቸው ቤተክርስቲያን ማለት እግዚአብሔር በሥርዓት ሁሉ አስተካክሎ የመሠረታት ናት ስለዚህ ሁላችን አብረን በነበርን ጊዜ አምላካችን እግዚአብሔር እንዳዘዘን ሊያደርጉላችሁ የምትፈልጉትን እናንተም አድርጉላቸው

ለቢጽክሙ::

111\. እስመ ከመዝ ይቤ እግዚአብሔር ሙሴኒ ነገሮሙ ለደቂቀ ፳ኤል ወይቤሎሙ ኢታምፅኡ እምዘባእድ እሳት ከመኢትሙቱ እንትሙኒ ኢታምፅኡ ጋእዘ ውስተቤተክርስቲያን ቅድስት

112\. በከመ እሙንቱ እሳተ አምፅኡ አምባእዳን ወሞቱ ወካዕበ ለእመ ተዓደው በዕበዶሙ ላዕለመምህሮሙ በከመ ተአደው ዳታን ወአቤሮን ወደቂቀቆሬ ወአብቀወት ምድር አፍሃ ወውሕጠቶሙ እሙንቱሰ እለኢኮኑ ቅቡአነ ውስተ እንቲአነ ቤተክደርስቲያን ቅድስት ወኢተወልዱ ዳግመ በቅድስት ቤተክርስቲያንእም ቅድስት ጥምቀት::

113\. አንትሙኒ እምድሕረ ተጠመቅሙ ለእመኢያስነይክሙ መልእክተክሙ ትወርዱ ውስተ ኵነኔ ነደእሳት እንተአልበቲ ሙጻእ እስከ ለዓለም::

114\. ወአንተኒ ኦ ወልድየ ቀሌሚንጦስ ኵኖሙ አርአያ ለብዙሐን ወአርእዮሙ ዘንተ ዘትገብር ሠናየ ከመይትመሐሩ ምግባሪከ ወኢታስተአኪ መርዔተ እግዚአብሔር ወሱቆሙ ለእለተንተኑ::

115\. ወአንስእሙ ለእለ ወድቁ ወባልሆሙ ለግፉዓን ወአናሕሲ አበሳሆሙ ወጌጋዮሙ:: ወኩኖሙ አርአያ ለሄራን ወለእኩያን ገሥፆሙ ከመ ይትገሐሱ እምእኩይ

111\. እግዚአብሔር ለእስራኤል ልጆች ከባእድ ሰው እሳትን አታምጡ እንዲህ ካደረጋችሁ ትሞታላችሁ ብሎ በሙሴ በኩል እንዳዘዛቸው ታውቃላችሁ ስለዚህ እናንተም በቤተክርስቲያን ላይ ክርክርን አታንሱ

112\. እስራኤላውያን የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ተላልፈው ከባእድ እሳትን ስላመጡ ሙተዋል በዚህም አካሄድ በዕብደታቸው እንደ ዳታንና እንደ አቢሮን በመምህሮቻቸው ላይ የድፍረትን አካሄድ ከተከተሉ እንደነሱ ምድር አፏን ከፍታ ልትውጣቸው ትችላለች ከቅድስት ጥምቀት ተወልደው የቤተክርስቲያን ልጆች ሳይሆኑ በድፍረት አይግቡ::

113\. እናንተም ከተጠመቃችሁ በኋላ ተልእኳችሁን በትክክል ካልተወጣችሁ እስከዘለዓለሙ መውጫ ወደሌለው ነደእሳት ኩነኔ ትገባላችሁ::

114\. ልጅ ቀሌሚንጦስ ሆይ አንተም ለብዙዎች አርአያ ትሆን ዘንድ ይገባል መልካምን ስራ ራስህ እየሠራህ ለሌሎች አሳያቸው እነሱ ያንተን መልካም ሥራን መሥራት እየተከተሉ ትምህርት ያግኙ ደካሞችንም ደግፋቸው::

115\. የወደቁትን አንሳቸው የተገፉትንም አድናቸው በደላቸውንና ክፋታቸውንም ይቅር በል ለደጋግ ሰዎች አርአያ ሁናቸው ክፉዎችን ደግሞ ገሥፃቸው ከክፉ ተግባራቸው ይርቁ ዘንድ

ወኢይግበሩ ዓመፃ በውስተ ፍትሕ ወበእንተ ቤተክርስቲን እንተአነ ንቤይን በርትዕ በከመአዘዘነ ወሠራዕነ ቀኖና ለቤተክርስቲያን

116. ወፈድፋደ ከመይትአቀቡ እምሰሚዓሐሰት ወእምዝሙት ወእም ሐዊረ ብእሲተ ብእሲ ወእማውታ በበትክ ወእም ሰዊዕ ወዘቢሕ ለአማልክት ወኢታርኩሱ ቅድሳቶ እስመ እግዚአብሔር ቅዱስ ውእቱ በከመይቤ ለሊሁ ቅዱሳነ ኩኑ እስመአነሂ ቅዱስ አነ።

117. ወኢትትናገሩ ዕርፈተ ላእለቢጽክሙ እስመበዕርፈት ወድቀ ሁይጣን እመንበሩ። ሚካኤልኒ ሊቀመላእክት በትሕትናሁ ተለዐለ እመንበሩ እንዘነፋሄቀርን ውእቱ እምኩሎሙ መላእክት ተለዓለ።

118. ወከማሁ ካህንሂ ዘቤተክደርስቲያን ይኩን ትሑተ ወየዋሃ ዘያሴኒ አበሳ ለጊጉያን ወይመይጦሙ በቃለ ሰላም ለመአስባን። ዝኬ ውእቱ ላእከ ክርስቶስ ገባራዊ ዘይመትር ቃለ እግዚአብሔር በርትዕ ከመመላፂ በሊሕ ዘ፪ አፉሁ

119. አው ሐረሳዊ ዘኢያፀንን ትልሞ የማነ ወጸጋመ እስመ

በፍርድ ጊዜም በደል እንዳይፈፅሙ ነገራቸው በቤተክርስቲያን ቀኖና ሠርተናል ስለዚህ በዚሁ ቀኖና እየተመሩ በቤተክርስቲያን ሥር ይኑሩ።

116. በይበልጥ ግን ሐሰትን ከመስማት ከዝሙት ከወንድ ሚስት ዘንድ መሄድ የበከተውን ከመብላት፣ ለጣዖት መሥዋዕትን ከመሰዋት ይጠበቁ የእግዚአብሄርንም የተቀደሰውን ተፈጥሮ አያርክሱ እግዚአብሔር ቅዱስ ነውና ራሱ ጌታችን ኢየሱስክርስቶስም እኔ ቅዱስነኝና እናንተም ቅዱሳን ሁኑ ብሏል።

117. በባልእንጀራችሁ ላይ ስድብን አትናገሩ ዲያብሎስ በስድብ ከመንበሩ ወድቋልና የመላእክት አለቃ ሚካኤልም በትሕትናው ከመንበሩ እጅግ ከፍ አለ የቅዱስ ሚካኤል ሊቀመላእክት ብዛት ከመንበሩ እጅግ ከፍ አለ የቅዱስ ሚካኤል ሊቀመላእክት ዋና ተግባሩ ነጋሪትን መምታት ነበር በትሕትናው ግን የዲያብሎስን መንበር ወረሰ።

118. እንዲሁ ካህንም የቤተክርስቲያን አገልጋይ ስለሆነ አስተዋይ የዋህ የበደለኞችን ጥፋት የሚያስዝብ በደለኞችን በቃለሰላም ወደቤተክርስቲያን የሚመልስ መሆን ይገባዋል። ካህን የክርስቶስ መላእክተኛና ገበሬ መሆኑን አይርሳ ካህን ሁለት አፍ ያለው ምላጭ ማለት ስለሆነ በእግዚአብሔር ቃል የሠይጣንን ተንኮል ይቆርጣል።

119. እንዲሁም ካህን ፈሩን አስተካክሎ እንደሚያርሲ ገበሬ፣ መሆን

ርትዕት ይእቲ መንግሥተ እግዚአብሔር ለእለይገብርዋ ዕቀቡ ዘንተ ትእዛዘ ከመኢትክሉ ምንሥዋነ እምእለ ይወርዱ ውስተግብ ዘውእቱ ሲኦል ወከመ ይድሐኑ መሐይምናን እምዘሀሎ ድልወቶሙ ለሐዋእን።

## ምዕራፍ ፱

## ትምህርት መንፈሳዊ እምኀበ ጴጥሮስ ሊቀሐዋርያት

1. ይቤ ጴጥሮስ ንሕነ ፲ ወ ፪ ሐዋርያት እንዘሀሎነ አሐተኔ ሕቡረ አነ ጴጥሮስ አዘዝኩ ከመዝ ለኩሉ ሰብእ ዘኢትፈቅድ ይግበሩ ለከ አንተሂ ኢትግበር ዲበ ቢጽከ እስመዝንቱ ኩሉ ኦሪትነ ወነቢያትነ ወንሕነ አዘዝነ ከመ ይዕናዕ ሃይማኖትክሙ።

2. ወዮሐንስ ፍቁሩ ለእግዚእነ ይቤ አሌ ሎቱ ለዘአርኰሰ ሥጋሁ በፍትወተዝሙት እስመ ሥጋሁ አባሉ እግዚአብሔር ይእቲ እምድሕረ ነሥአ ጥምቀተ ወዘተ መጠወ ሥጋሁ ወደሞ ለክርስቶስ ይከውን ፩ ነፍስ ወ፩ሥጋ ምስሌሁ እምድሕረ ነሣእክሙ አባለ ክርስቶስ ትሬስይዎኑ ለሥጋክሙ አባለዘማ ሐሰ።

አለበት ገበሬ በእርሻው ጊዜ ፈሩን ግራና ቀኝ ሳያማምም ያርሳል የእግዚአብሔር መንግሥት የቀናች ናት የእግዚአብሔርን መንግስት ጠብቁ እንዳትጠፉ ወደ ሲኦልም እንዳትወርዱ ምእመናን ሐጢአተኞች ሊገቡበት ከተዘጋጀው ገሀነም እንዲድኑም አስተምሩ

## ምዕራፍ ዘጠኝ

## ከሊቀሐዋርያት ጴጥሮስ የተሠጠ መንፈሳዊ ትምህርት

1. ቅዱስ ጴጥሮስ እንዲህ ይላል "እኛ ሐዋርያት አሥራሁለት ሁነን ተሰብስበን ሳለ ፣ አንድ ድምፅ የሚከተለውን መልእክት አስተላለፍን" ሰው ሁሉ በራሱ ሊፈፀምበት የማይፈልገውን በሌላውላይ ማድረግ ከክርስቲያናዊነት ያስወጣል ይህንን ሁሉ አሪትና ነቢያት ይከለክላሉ እኛም ሀይማኖታችሁ የፀና ይሁን እንላለን።

2. የጌታችን ወዳጅ ዮሐንስም ሥጋውን በዝሙት ለሚያረክስ ሰው ወዮለት የሰው ሥጋ ቤተክርስቲያን አባል ለመሆን በጥምቀት ዳግም ልደትን ካገኘች ጀምሮና ኢየሱስክርስቶስ ሥጋንና ደምን ከተቀበለች ጀምሮ በነፍስና በሥጋ ከኢየሱስ ክርስቶስ ጋር አንድ ናትና የክርስቶስን አንድነት ከተቀበላችሁ በኋላና የሱምአካል ከሆናችሁ በኋላ ሥጋችሁ የዝሙት አካል ታደርጉታላችሁን

3. ኵሉ ብእሲ ይንበር በብእሲቱ ወብእሲትኒ ትንበር በምታ ወካዕበ ይቤ እሁነ ጳውሎስ እመሰ አውሰብከ ብእሲተ ኢትትፈለጥ እምኔከ ብእሲትከ ወእመሰ ተሐድጋ ትንበር በከ ወይሄይስ እመነበረት በምክርየ ወካዕበ ይቤ እመሰ አልብከ ብእሲት ኢትፍቅድ አንስተ ከመኢይኩንከ ኀጢአተ።

4. እስመ ይኄይስ አውስቦ እምዘምዎ ወዘይዜሙ ኀበ እንተኢኮነት ብእሲቶ ከመ ዘይሠውዕ ደመ ለአጋንንት ወይትኴነን በደሐሪት እለተ ደይን እመሐረ በፍኖተ ሠይጣን ዘራኤ እኪት ውስተ አልባበ ሰብእ ዘኢይፈቅድ ከመይድኀን ፩ሂ እምኔነ።

5. ወቀርነስ ለሠይጣን ትዕቢት ወትዝሕርት ወሐምየቢጽ ሥሥዕት ወስትይ ወሥካር ወዝሙት ወመሐላ በሐሰት ወበአፍ ተዛልፎተ ቢጽ ወበቃለ ስሕተት ወዘይመስሉ ምግባረእ ኪት ወተቃዕቦ ወስሐቅ ወትውዝፍት ወላኲ ወመዓት ወሐይድ ንዋየ ባእድ ወሠሪቅ ወሐዊረ ብእሲተ ብእሲ።

6. ወፀሊአቢጽ ምግባር እኩይ ዘዘርአ ሠይጣን ውስተ ልበሰብእ ወዘርኡስ ለመንፈስ ቅዱስ ዝ ውእቱ ትሕትና ወየውሃት ወፍቅር ወሰላም ጾም ወጸሎት ወምሕረት ወስኢል

መሆን የለበትም ብሏል።

3. ሰው ሁሉ ባንዲት ሚስት ፀንቶ ይኑር እንዲሁም ወንድማችን ጳውሎስ እንዲህ አለ "ሚስት ካገባህ ጀምሮ ከሚስትህ ተለይተህ በሌላ ቦታ ብዙ አትቆይ ከባል የተለየች ሴት ካለች ብቻዋን ትኑር ሁላችሁም እኔ በሠጠሁዋችሁ ምክር ብትኖሩ ይሻላችኋል ሚስት ከሌለህ ብዙ ሴቶችን መመልከት የለብህም ይህን ካደረግህ ኃጢአተኛ ነህ" ብሏል።

4. በሕሊናውም ሆነ በተግባሩ እያመነዘረ ከሚኖር ሚስት አግብቶ የሚኖር ይሻላል ሚስቱ ካልሆነች ሴት ጋር የሚያመነዝር ሰው ለአጋንንት የእንስሳትን ደም እንደሚሰዋ ሰው ይቆጠራል በፍርድ ቀንም ፍዳውን ይቀበላል በሠይጣን መንገድ ተጉዟልና ሰይጣን ከኛ አንዱ ሰው እንኳ እንዲድን አይፈልግም።

5. የሠይጣን ዘሩ ትዕቢት ትዝህርት ባልንጀራን ማማት፣ ሥሥዕት፣ መጠጥ ስካር፣ ዝሙት፣ በሐሰት መማል፣ ባልንጀራን መዝለፍ፣ በተሳሳተ ቃል ስሕተትና የመሳሰለው ሁሉ ነው መጠቃቀስ፣ መሳቅ፣ ቊጣ፣ ምቀኝነት፣ መሥረቅ፣ ወደ ወንድ ሚስት መሄድም የሠይጣን ናቸው።

6. ባልንጀራን መጥላት ጨምሮ ከዚህ በላይ የተዘረዘሩት ሁሉ የሠይጣን ዘሮች ናቸው መንፈስቅዱስ በሰው ልቡና የሚዘራቸው ዘሮች ግን ትህትና፣ የዋህነት፣ ፍቅር፣ ሰላም፣ ጾም፣ ጸሎት፣

ወአንብቦ ወምሒረነዳይ ወምዕዋት ዝ ኩሉ ፍቅር ዘይዘርእ መንፈስ ቅዱስ ውስተ ልበሰብእ።

7. ጠቢባን ከመ ይግበሩ ወይዕቀቡ ትእዛዘ እግዚአብሔር ወኢይሑሩ በፍኖተ ሠይጣን ከመኢይሥርቅ ሕሊናሆሙ ፩ ጊዜ በፍሥሐ ወ፩ ጊዜ በትካዝ ወለፍሥሐክሙ ሚጥዎ ውስተብካይ ወሐዘን ወለሐዘንክሙኒ ተወከፍዎ በአኮቴት ከመይትፌሳህ እግዚአብሔር ብክሙ።

8. ወይፌድየክሙ ኵሎ ሠናያተ ዘዓይን ኢርእየ ወእዝን ኢሰምዓ ውስተ ልበሰብእ ዘኢተሐየ ዘአስተዳለወ እግዚአብሔር ለእለ ያፈቅርዎ እስመ ኢርእያ ዓይነሰብእ ወኢሰምዓ ዕዝነ ሰብእ ለእንተ ተደለወት ለኄራን ገነተ ትፍሥሕት።

9. አልቦ ዝየ ሐዘን ከመትባኡ ህየ ዕቀቡ ሥርዓተ መላእክት ምእመናን ዘተውህበ እምንበእግዚአብሔር ኢየሱስ ክርስቶስ ከመትዕቀቡ ሕጋ ወሥርዓታ ለቅድስት ቤተክርስቲያን ወእለሰ ኢአቀቡ ህጋ ወሥርዓታ ይትኌለቁ ምስለ መዓሥባን ወመናፍቃን።

10. ወለእለሰ ዐቀቡ ሕጎ ወሥርዓቶ ይሁቦሙ ዓሥቦሙ ከመይንሥኡ ዓስበየማሆሙ እስመ አስተፍሥሕዎ

ይቅርባይነት፣ ሥዕለት፣ ለድሐ መራራት፣ ምዕዋት፣ ሲሆኑ እነዚህ ሁሉ ሕይወቱን ለመንፈስቅዱስ የሠጠ ሰው የሚያገኛቸው ናቸው።

7. ብልሆች የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ይጠብቁ ዘንድ በሠይጣንም መንገድ እንዳይሄዱ በደስታ አንድጊዜ በሐዘንና በትካዜ ሌላ ጊዜ ሠይጣን ልባቸው እንዳይሠርቅ ይጠንቀቁ እናንተም ደስታችሁን ወደሐዘንና ወደትካዜ ለውጡት ሐዘናችሁንም በአኮቴት ተቀበሉት እግዚአብሔር በናንተ ደስ ይለው ዘንድ።

8. ይህን የመሰለ ሕይወት ካላችሁ ዓይን ያላየውን ጆሮ ያልሰማውንና በሰው ልቡና ያልታሰበውን እግዚአብሔር ይሠጣቹኋል ገነተትፍሥሕት የሰው ዓይን ያላያት ናት የሰው ጆሮም ያልሰማት ናት ስለዚህ ለዚህ ትልቅ ጸጋ ትበቁ ዘንድ ትጉ።

9. በገነተትፍሥሕት ሐዘን የለም ወደዚሁ ለመግባት ትችሉ ዘንድ ከጌታችን መድሐኒታችን አምላካችን ኢየሱስ ክርስቶስ እግዚአብሔር ዘንድ ለምዕመናን መላእክት የተሠጠውን ሥርዓት ጠብቁ የቅድስት ቤተክርስቲያንን ሥርዓት በመጠበቅ ይህንን ታገኛላችሁ ከዚህውጭ ከሆናችሁ ግን ከመዓሥባንና መናፍቃን ጋር ትቆጠራላችሁ

10. እግዚአብሔር ህጉንና ሥርዓቱን ለሚጠብቁ ሁሉ ምሥጋናቸውንና ዋጋቸውን ይሠጣቸዋል የድካማቸውንም ዋጋ

ለመርዓዊ ስማያዊ በምግባር ቅዱስ ዘዕድቅ እስመ ሀበሀሎ መንፈስጽድቅ ህየ ሀሎ መንፈስ ግእዛን እስመ መንፈስጽድቅ ታግእዝ ኩሎ ዘይገብር ኃጤአተ፡፡

11. እመሰ ጽድቅ ታግእዘክሙ አማን ግኡዛን አንትሙ ወተመነንክሙ እምኀበጽድቅ እስመበፈቃድክሙ ገበርክምዋ ለኀጢአት ወእምግብርናት እንዘ ትሬእዩ ኩሎ ዘቤተክርስቲያን እስመተብህለ ቤተ ክርስቲን ብሂል ነፍሰክርስቲያን ብሂል ወመንፈስ ክርስቲያንሂ መንፈስክርስቶስ ውእቱ፡፡

12. ወመንፈስክርስቶስ መንፈሰእግዚአብሔር ኀበሀሎ ይግእዝ ኃጢአት ወመንፈሰ እግዚአብሔር ትፀርህ ላእለብእሲ ጻድቅ እንዘተብል መሐረነ እግዚአብሄር ወተሠሀለነ.

13. ወእንዘ ይብል ከመዝ ወይፀርህ ጻድቅ ብእሲ ኢይኤብስ እስመእግዚአብሔር ሀሎ ላእሌሁ ውስተሕሊናሁ ወበእንተዝ ይሴውሮ እምሥህተተ አጋንንት ንትዓቀብ እምስሕተተ አጋንንት እንዘሀሎ መንፈሰእግዚአብሔር ላእሌነ ወናሠንያ ለቤተክርስቲያን በከመ አዘዙነ ሐዋርት እንዘ ነአትት ደዌያተ ነፍስነ ወሥጋነ፡፡

ይከፍላቸዋል ሰማያዊውን ሙሽራ በተቀደሰ አካሄዳቸው ደስ አሰኝተውታልና የዕድቅ መንፈስ ባለበት በዚያ ነፃነትና ደስታ መንፈስ አለና መንፈስ ጽድቅ ከሐጢአት ነፃ ታወጣለችና፡፡

11. እውነት ነፃ የምታወጣችሁ ከሆነ እናንተ በእውነት ነፃነትን የተቀዳጃችሁ ናችሁ ሐጢአትን ለመሥራት የሚያስገድዳችሁ የለም በገዛፈቃዳችሁ ብቻ ሐጢአትን ትሠራላችሁ ካሁን ጀምሮ ግን ነፃ የወጣችሁ ሁኑ ሐጢአት አይግዛችሁ የቤተክርስቲያንን ሥርዓት ሁሉ ተመልከቱ ቤተክርስቲያን ማለት የክርስቲያን ነፍስ ማለት ነው የክርስቲያን ነፍስም የክርስቶስ ነፍስ ማለት ነው፡፡

12. ኃጢአት ሊወገድ ካለበት ዘንድ ኢየሱስ ክርስቶስ የእግዚአብሔር መንፈስ እንዲህ እያለች ድምፂን ታሰማለች፡፡ የምታሰማውም በፃድቅ ሰው ላይ ነው፡፡ ድምፅዋንም የምታሰማው እግዚአብሔር ሆይ ማረኝ ይቅርም በለኝ እያለች ነው፡፡

13. እንዲህ እያለ ሲጮህ ጻድቅ ሰው በሐጢአት አይቸነፍም (ወድቆ አይቀርም) እግዚአብሔር በሱ ላይ አለና ሕሊናውም ሁሉ ከእግዚአብሔር አይርቅምና እግዚአብሔርም የሕሊናው ቅንነት እያየ በአጋንንት እንዲረገጥ አሳልፎ አይሠጠውም ስለዚህ ሁላችን ከአጋንንት ስህተት እንጠበቅ ከሥጋና ከነፍስም ደዌ እየተጠበቅን ሐዋርያት አባቶቻችን እንዳዘዙን ቤተክርስቲያንን እንጠብቃት፡፡

14. ወእምዝ እመኢመራሕክምዎሙ ለሕዝብ እለእምታሕቴክሙ ወኢነገርክምዎሙ ይወቅሰክሙ እግዚአብሔር እስመይቤሎ እግዚአብሔር ለሕዝቅኤል ነቢይ ወልደ እግዚአብሔር ወልደ እጓለእመሕያው ረሰይኩከ ሰብአዓይን ላዕለሕዝብ

15. ንግሮሙ ለኃጥአን ይነሥሑ እምሐጢአቶሙ ወእመሰነገርኮሙ ወኢነሥሑ እም ሐጢአቶሙ ይመውቱ በሐጢአቶሙ ወእመሰ ነገርኮሙ ወነስሑ እምኀጢአቶሙ አድሐኮ ርእሶሙ አንተኒ ትትአሰይ በኀበእግዚአብሔር ወካዕበ ንግሮ ለፃድቅ ከመኢይትመየጥ ኀምዕድቁ።

16. ወእመሰ ገብረ በከመአዘዝኮ አድሐነ ርእሶ ወእመሰ ነገርኮ ወኢተዓገሠ በፅድቁ ይመውት በኃጢአቱ አንተሰ አድሐንከ ርእስከ ወእመሰ ዐቀበ ጽድቆ እስከዕለተ ሞቱ ይመውት በፅድቁ ወይትአሰይ በኃቤየ አንተኒ ትትአሰይ በኃቤሁ ሀየንተዘገበርከ ወነገርኮ።

17. ከመዝ አዝዞሙ ለካህናት ከመይንግርዎ ለሐጥእ ይነሥህ እምሐጢአቱ ወኢያድሉ ለገፅ ወኢይፍርህዎ ለባዕል በእንተ ብዕሉ ወኢለንጉሥ በእንተ ዕበየ ክብሩ እስመ ንጉሠሰማያት ወምድር ዘላእሌሁ ለውእቱኬ ያከብሮ

14. በዚህም አካሄድ ሕዝቦችን ካልመራቿኋቸው ከኛ ሥር ሁነውም እያለ ከማስተማር ችላካላ ችኋቸው እግዚአብሔር ይወቅሳቿኋል እግዚአብሔር አምላክ ነቢዩን ሕዝቅኤልን እንዲህ ብሎታል የሰው ልጅ ሆይ በሕዝብ ዘንድ የዓይን ምሥክር አደረግሁህ።

15. ሐጢአተኞችን ንሥሐ ይገቡ ዘንድ ንገራቸው (ከስሕተታቸው ይመለሱ ዘንድ) አንተ እንዲመለሱ ነግረሃቸው ካልተመለሱ ግን በዚሁም ከሞቱ አንተ ራስህን አዳንክ እነሱም በኃጢአታቸው እንደሞቱ ይቀራሉ ወይም ደግሞ አንተ ስላስተማርካቸው ከተመለሱና ንሥሐ ከገቡ ከኃጢአታቸውም ከራቁ ራሳቸውን ካዳኑ አንተ ከእግዚአብሔር አምላክህ ብዙ ሥጦታ አለህ ጻድቁንም ቢሆን ከፅድቁ ወጥቶ እንዳይጠፋ አስተምረው።

16. አንተ እንደ ነገርከው ባንተ ተመርቶ መልካም ከሠራ ራሱን አዳነ ካልተመለሰ ግን ኃጢአቱን ተሸክሞ ይሞታል አንተ ግን ሐላፊነትህን ተወጥተሃል። ባንተምክር ተጠብቆ እስከዕለተሞቱ ድረስ ከቆየ ጽድቁንም ከጠበቀ ከኔ ዘንድ መልካም ሥጦታ አለው አንተም እሱን አስተምረህ በመመለስህ ዋጋህ ብዙ ነው።

17. ለካህናት ከእግዚአብሔር የታዘዘው ይህ ነው ካህናት ሐጢአተኛው ንሥሐ እንዲገባ ብዙ መድከም ሥራቸው ነው ይህንን ሲያደርጉ ፊቱን በማየት እንዳያዳሉ ይጠንቀቁ ንጉሥም ይሁን ሌላ ባለሥልጣን ሥጋዊክብሩን ከስብእናው ለይተው

ክርስቲያን ይቤ እግዚአብሔር ለዘአፍቀረኒ ወዓቀበ ትእዛዝ
አሬቅሮ።

22. ለዘሰ ይፀልእ ቃልየ ወኢአቀበ አኮ አነ ዘእኳንኖ አላ ውእቱ ቃልየ ይኳንኖ ወስምዓ ይከውን ቦቱ እመልእልተርእሱ ወይፀሐፍ ውስተ መፅሐፈ ዕዳሁ ወይትነበብ በቅድመ መላእክት ወሰብእ ሥርዓተ ቤተክርስቲን ከመ በእንተ ኢየሩሳሌም ሰማያዊት ከማሃ ይኩን ሥርዓታ ለእንተ በምድር ቤተክርስቲያን

23. ወአመ ዐርገ እግዚእነ ኢየሱስክርስደቶስ ውስተ ሰማያት እምድሕረ ወሀበነ ሥርዓታ ለቅድስት ቤተክርስቲን ወበቀ ኅሚት ዕለት ሰበዓርገ እምነቤነ ሐዋርት መሀሮሙ ለእለ ውስተ አየር መላእክት

24. ወበዳግሚት ሰለት መሀሮሙ ለሊቃነመላእክት ወሰገዱ ሎቱ ወአምኑ ቦቱ ከመውእቱ እግዚኦሙ ምስለውእቱ ሥጋነ እንተነሥአ እምኔነ ወዓርገ። ወበሳልስ መሐሮሙ ለኢጋእዝት ወእሙንቱ ሰገዱ ሎቱ ወአምኑ ቦቱ ከመውእቱ እግዚኦሙ ምስለ ውእቱ ሥጋነ እንተነሥአ እምኔነ ወዓርገ።

25. ወበራብዕ ዕለት መናብርት አምኑ ወሰገዱ ሎቱ ምስለውእቱ ሥጋ እንተነሥአ እምኔነ ወዓርገ ወበሐምስ ዕለት መሐረ ሐይላተ ወአምኑ ወሰገዱ ሎቱ ከመውእቱ እግዚኦሙ

የሠጠሁትንም ሕጌ ከተደፋፈርከ ስምህን አጠፋለሁ ትእዛዜን ለጠበቀ ሁሉ እወደዋለሁ።

22. ቃሌን የሚጠላና የማይጠብቀው እኔ አይደለሁም የምኰንነው ያ ከሱ ፊት ሲነገር የኖረው ቃሉ ይፋረደዋል ምሥክርም ይሆንበታል በግሉ ዕዳመጽሀፍም ይፃፍበታል ካህን የሆነ ሁሉ በሰማያዊቷ ኢየሩሳሌም ሥርዓት አስመስሎ ምድራዊቷን ቤተክርስቲያን በአለቆች ፊትና በሰውም ሁሉ ፊት ይፈፅም።

23. ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከኛ ከሐዋርያት ተለይቶ ወደሰማያት ከማረጉ አስቀድሞ የቤተክርስቲያንን ሥርዓት አስተምሮናል ወደሰማይ በአየር ላይ የሚኖሩትን መላእክት አስተምሮአቸዋል።

24. በዳግም ዕለትም ሊቃነመላእክትን አስተማራቸው እነሱም ሰገዱለት በሱም አመኑ ጌታቸው መሆኑንም አምነው አወቁት መላእክት ከኛ የለበሰውን ሥጋ እንደለበሰ አዩት ከዚሁ ሥጋ ጋር አርጓልና በሦስተኛ ጊዜ አጋእዝትን አስተማራቸው እነሱም አምነው ሰገዱለት ከኛ ለብሶት ያረገውንም ሥጋ እንደለበሰ አዩት።

25. በአራተኛው ዕለት ከኛ የለበሰውን ሥጋ ይዞ ሲያርግ አይተው መናብርት አመኑ ሰገዱለትም በአምስተኛው ዕለት ኃይላትን አስተማራቸው እነሱም ከኛ የለበሰውን ሥጋ ይዞ ሲያርግ

ምስለውእቱ ሥጋ እንተነሥአ እምኔነ ወዓርገ።
26. ወበሳድስ ዕለት መሐረ ሊቃናተ አምኑ ወሰገዱ ሎቱ ከመውእቱ ሥጋ እንተነሥአ እምኔነ ወዓርገ ወበሳብዕ ዕለት መሐረ ኪሩባውያነ ወአምኑ ወሰገዱ ሎቱ ምስለ ውእቱ ሥጋ እንተነሥአ እምኔነ ወዓርገ።

27. ወበሳምንት ዕለት መሐረ ሱራፌላውያነ ወሰገዱሎቱ ወአምኑ ከመውእቱ እግዚእሙ።
28. ወበታሥዕ ዕለት መሐረ መኳንንተ ወእሙንቱ አምኑ ከመውእቱ እግዚእሙ ወሰገዱ ሎቱ ምስለውእቱ ሥጋ ዘነሥአ እምኔነ
29. በበዕበዮሙ ወበበነገዶሙ በበማህበሮሙ ወበበዖታሆሙ ምስለ ውእቱ ሥጋ እንተነሥአ እምኔነ ወዓርገ። ወበዓሥር ዕለት ነበረ ውስተመንበረ መለኮቱ በየማነ አቡሁ ስቡሕ ወአውረደ ለነ ጰራቅሊጦስሃ መንፈስቅዱሰ ዘይምሕረነ ኩሎ መንፈሰ ጥበብ ወአእምሮ።

30. ወአሜሃ ተናገርነ በነገረኩሉ በሐውርት ወተካፈልነ ዓለመ በምልዐ ከመንስብክ ወንምሐር ወነበርነ አሐተኔ ወሠራዕነ ቤተክርስቲያነ እንተ በኩለሄ ወወዓዕነ ከመንስብክ ዜናወንጌል ቅዱስ ውስተኩሉ ዓለም

በማየታቸው ጌታቸው መሆኑን አምነው ወደሱ ሰገዱ
26. በስድስተኛው ቀን ሊቃናትን አስተማረ እነሱም ወደሱ ሰገዱ እሱ ጌታቸው መሆኑንም አመኑ ከኛ የለበሰውን ሥጋ ለብሶ አይተውታልና በስድስተኛው ዕለት ኪሩባውያንን አስተማረ። እነሱም እሱ ጌታቸው እንደሆነ አውቀው ሰገዱለት አመኑም የለበሰውንም ሥጋ አዩ።
27. በስምንተኛው ቀን ሱራፌልን አስተማራቸው እነሱም ጌታቸው እንደሆነ አመኑ ሰገዱለትም።
28. በዘጠነኛው ቀን መኳንንትን አስተማራቸው እነሱም አመኑ ሰገዱለትም ከለበሰው ሥጋ ጋር አይተው ጌታቸው መሆኑን አውቀዋልና።
29. ሊቃነ መላእክት በየነገዳቸውና በየማደርያቸው በየወገናቸው ሁነው ከዚያ ከኛ ከነሳው ሥጋ ሁኖ ሲያርግ አስተማራቸው ካስተማራቸውም በኋላ በአሥረኛው ቀን በመለኮቱ ተቀመጠ ባባቱ ቀኝም ተቀመጠ ከዚሁ ቀጥሎ በዚሁ ዕለት መንፈስቅዱስን ላከልን እሱም ይመራናል ጥበብንና የአእምሮን መንፈስንም ያሳድርብናል።
30. በመንፈስቅዱስም ያንጊዜ በብሄሮች ሁሉ ቋንቋ መናገር ቻልን ዓለምንም ሁሉ ወንጌልን እንሰብክና እናስተምር ዘንድ ተበታተንን መንፈስቅዱስም ሲወርድልን አንድ ላይ ተሰባስበን እንገኝ ነበር የቤተክርስቲያንንም ሕግና ሥርዓት ሠራን።

31. ወከመ ያዕንዐ ሃይማኖተ ወይንበሩ በህገቀኖና በከመ ሠራዕነ ቀዲሙ ከመይኩኑ ትጉሓነ ለቤተክርስቲን ቤተ እግዚአብሔር ወመስተሐምማን ለግብረ ቅድስና ወንቁሐነ ለጸሎት በዘይደሉ ለቤተእግዚአብሔር፡፡

32. እስመ ሐና ነቢዪት ወለተ ፋኑኤል እንተ እምነገደ አሴር ኢየዓርፍ ከናፍሪሃ እምስብሐተ እግዚአብሔር መዓልተ ወሌሊተ ወአዲ ከናፍሪሃ ኢይትሐወስ ወቃላ ኢይሰማዕ ወከማሁ ይደልዎሙ ለመሐይምናን ይጸልዩ ወትረ በውስተ ቅድስተ ቅዱሳን በእንተ መድሐኒተ ነፍሶሙ፡፡

33. እስመዘይዔሊ ለእግዚአብሔር በንፁሕ ልብ ውእቱኬ ይነሥእ ሠናየ ዘአስተዳለወ ለእለያፈቅርዎ

34. ኦ. ወልድየ ቀሌሚንጦስ ስማዕ ዘእነግረከ ለእለይትሜየንዎ ለቃለ እግዚአብሔር አልቦሙ መክፈልት ውስተቅድስት ቤተክደርስቲን እንተሐዋርያት፡፡ ረሰይናሃ ለቤተክርስቲን ምስለ ሰማይ እስመሰማያዊት ይእቲ ወያስተርኢ በላእሌሃ ብርሃን ከመፀሐይ እምርሑቅ ከመ መድበለ ማሕበር፡፡

35. ወአዲ ርእዩዋ ነቢያት እንዘ ውስተ ገዳም ትነብር ወታስተሐውዝ ውስተ አርእስተ አድባር ወነሳእናሃ ትኩነነ ርእሰ ውስተ ዘዚአሁ ክብር ወንሕነሂ በከመ አዘዘነ እግዚእነ ሠራዕነ በውስቴታ

31. የምናስተምረውም ሕዝቦች እኛ በምንመሠርተው ሥርዓት እየተመሩ እንዲኖሩ ለቤተክርስቲያንም እንዲተጉ ቤተእግዚአብሔርም በነሱ እንድትገለገል እናደርጋለን ሕዝቦች ለቅድስና ሥራና ለፀሎት የተጉ እንዲሆኑም እናደርጋለን፡፡

32. ከአሴር ወገን የሆነችው የፋኑኤል ልጅ ሀና ፀሎት ከማድረስ በፍፁም አታርፍም በከንፈርዋ እግዚአብሔርን ስታመሰግን ትኖር ነበር ሐና ሌት ተቀን ከእግዚአብሔር ምስጋና አታቋርጥም ከንፈሮቿ ሲላወሱ (ሲንቀሳቀሱ) አይታይም ለመሐይምናንም እንዲሁ መሆን ይገባቸዋል መሐይምናን የሚፀልዩትም ስለነፍሳቸው ነው፡፡

33. በንፁሕ ልቦና ወደእግዚአብሔር የሚፀልይ እግዚአብሔር ለወዳጆቹ ያዘጋጀውን መልካም ሰማያዊ ሕይወትን ያገኛል፡፡

34. ልጄ ቀለሚንጦስ ሆይ የምነግርህን ስማኝ የእግዚአብሔርን ቃል ችላ የሚሉ ሁሉ ከቅድስት ቤተክርስቲያን ዕድል የላቸውም ቤተክርስቲያን የሐዋርያት ስለሆነች የሰማያዊቷ ኢየሩሳሌም ምሳሌናት እሷ ሰማያዊትናትና በሷም ላይ ብርሃን ከሩቅ እንደፀሐይ ይታያል እሱም የማሕበር መድበልን ይመስላል፡፡

35. ነቢያት ቤተክርስቲያንን በገዳም ውስጥ ሁና አይተዋታል በተለያዩ በተራሮች ላይ ሁናም እጅግ ስታምር ተመልክተዋታል በተለያዩ የመንፈሳዊ ክብሮችም የበላይ ትሆነን ዘንድ አደረግን ጌታችን እንዳዛዘንም በሷ ላይ ሥርዓትን ሠርተናል፡፡

36. ወአስተዳለውናሃ ለመርዓዊ ሰማያዊ በከመአዘዘነ ለሊሁ ወገበርነ ሠርዓተ፡ሃ ቀዳሚ ዘነቢያት ወዳግም ዘሐዋርት ዘዚአነ ወእምዝ ለሊቃውንት እለቤተክርስቲን ጳጳሳት ወእምዝ ለሕዝብ ወለኵሉ ደሴያት ወበሐውርት ከመይትፌሥሑ በሥርዓታ ለቅድስት ቤተክርስቲያን፡፡

37. ቤተክርስቲያን እንተአነ ይእቲ እንተ ቀደሳ በደሙ በዓተባ በዕፀ መስቀሉ ከመትኵን ምሥአለ ወምሥጋደ ወምስትስራየ ኵሉ ኃጢአት፡፡

38. እንተ ዕውበ ታቀልል ወዘተመንደበ ትረድእ ይእተኬ ንዕቀብ ሥርዓታ በኵሉ ጥንቃቄ እንዘ ናስተጥዕም ላተ በተድላ ወሃይማኖት ዘመንፈስቅዱስ በስብሐተ ዋህድ ወልደ እግዚአብሔር መድኀኒነ ወንሕነኒ ንትፌሳህ ባቲ ወእለፀንዑ በሥርዓትነ ይፌስሑ ፌድፋደ እስመ ቤተክርስቲያን ዘሕዝብ ይቤ ነፅሪ ዓውደኪ ወተፈስሒ በሕዝብኪ እለአርትዑ ነፍሶሙ በንስሐ እስመ ይተፌስሑ በውስቴታ፡፡

39. እስመ ነፍስክርስቲያን ወዓናቅጺሃ ኢይትዓወቅ እስመ ዓናቅጺሃ ለሊሁ እግዚእነ ዘቦአ እንተ ዓናቅጺሃ ወቦአ እንተደዴሃ ቤተክርስቲያን መንግሥተ ሰማያት ይእቲ ባቲ ንሄሊ እንዘ ነዓቅብ ትእዛዞ ለእግዚአብሔር፡፡

36. ጌታችን ባዘዘን መሠረትም ለሰማያዊው ሙሽራ እንድትሆን አዘጋጀናት የሷም ሽልማቶች በመጀመሪያ ነቢያት ቀጥሎ እኛ ሐዋርያት ከኛ ቀጥለው ሊቃውንትና ለቤተክርስቲያን በደሴቶች በብሄሮችና በአገሮች ላሉ ሕዝቦች ሁሉ ትሰጣለች ሕዝቦቹም በሷ ይደሰታሉ፡፡

37. ቤተክርስቲያን የኛ ገንዘብናት መድሐኔዓለም ክርስቶስ በደሙ ቀድሶና በዕፀመስቀሉ ባርኮ መስመኛና መስገጃ የሐጢአትም ማስተሠሪያ ትሆን ዘንድ ሠጥቷታልና

38. ቤተክርስቲያን ጭንቅን ታቀላለች የተቸገረውንም ትረዳለች እኛም የሷን ሥርዓት በጥንቃቄ እንጠብቅ መንፈሳዊውም ሁሉ በሷ እንዲሟላ እያደረግን እንኑር የመንፈስቅዱስ ፍሬም በሷ እንዲያፈራ እናድርግ ይህም በመድኃኒታችን አንድ ወልደ እግዚአብሔር ምስጋና ነው እኛ በሷ እንደሰት የኛንም ሥርዓት ጠብቀው በሷ የሚኖሩ እንደኛ ይደሰቱ ቤተክርስቲያን በሕዝብ ዘንድ ናት ቤታችን አደባባይሽን ተመልከቺ በሕዝብም ደስ ይበልሽ ብሏልና በንሥሐ ሕይወታቸውን አስተካክለው የተገኙትም ሁሉ በሷ ይደሰታሉ

39. ቤተክርስቲያንና በሮቿ አይታወቁም የቤተክርስቲያን በር ራሱ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ነውና በሱ አማካይነት ወደቤተክርስቲያን ይገባል በሯም እሱ ነው ቤተክርስቲያን መንግሥተሰማያት ናት የእግዚአብሔርን ትእዛዝ እየጠበቅን በሷ

40. እስመ ይቤ ለሊሁ አነ ውስቱ ዐንቀፅ ዘበአማንቱ ወአልቦ ዘይመፅእ ኀበአብ ዘእንበለ እንተ ሐቤየ ወዘኢያየ አእመረ አእመሮ ለአቡየ ዘፈነወኒ ይቤ አነ እሜሕሮሙ ለንዑሓን ወዘይበውዕ ኀቤየ ይረክብ ምርአየ ይበውእ ውስተ መርዓይ እንዘይትፌሣህ።

41. ወይቤ አነ ብርሃን ወአበርሕ አዕይንተ ዕውራን ወእነብር ወእዘብጦሙ ለአጋንንት ወአሰጥሞሙ ለመራእየ አሕርው ውስተባሕር።

40. ወይቤ አነ ሕይወት ወአነሥኦ ለአልአዛር እመቃብር እምድሕረ ረቡዕ ዕለት ይቤ አነ ውእቱ ዕፀ ሕይወት ወይቤ አነ ውእቱ ዐፀደ ወይን ወእሬስዮ ለማይ ወይነ ወአፀግብ እለ ውስተ ከብካብ ይቤ አነ ውእቱ ሕብስተ ሕይወት ዘወረደ እምሰማይ ወአፅገብ ኵሎ በ፭ ኀብስት ፶፻ ብእሴ ዘእንበለ አንስት ወደቅ።

41. ወይቤ አነ ውእቱ ነቅዓማይ ዘፀምዓ ይምፃእ ኀቤየ ወይስተይ ይቤ አነ ውእቱ ፀሐየ ፅድቅ ዘበአማን ዘያበርህ ውስተ ልበሰብእ መሐይምናን ፀሐይሰ ሠረቃ ተዓርብ ወክርስቶስ-ፀሐየ ፅድቅ ዘኢየዓርብ።

42. ይቤ አነ ሕይወት ወመድኀኒት አነ ማሕቶት ዘያበርሕ ዕልመተ ልብ ለእለ የዓቅቡ ትእዛዝየ። ወአበርሕ

እንኖራለን።

40. እሱ ራሱ እውነተኛ በር እኔነኝ ብሏል በኔ በኩል ካልሆነ ከአብ ዘንድ ማንም አይደርስም እኔን የሚያውቅ አባቱንም ያውቀዋል እኔን የላከኝ እሱ ነውና እሱ የንዑሐን የማደርያቸው ነው በር እኔነኝ ብሏል ወደኔ የገባ የሚሰማራበትን ያገኛል እየተደሰተም ይገባል።

41. ደግሞም የዕውራንን ዓይን የማበራ እኔነኝ በትርም እኔነኝ አጋንንትም እያረገፍኩ አባርራቸዋለሁና የአሳማ መንጋዎችንም ወደ ባሕር አሰጥማቸዋለሁ አለ።

40. እንዲህም አለ እኔ ሕይወት ነኝ አልአዛርን ሙቶ ከተቀበረበት በ4ኛው ቀን አስነሳሁት የሕይወት ዕፅ እኔነኝ የወይን ቦታም እኔ ነኝ ውሃውን ወይን አደረግሁት በሠርግ የተሰበሰቡትም ብዙ ሕዝብ ከወይኑ ጠጥተው ረኩ የሕይወት እንጀራም እኔ ነኝ ከሰማይ የወረድኩ የሕይወት እንጀራም ስለሆንኩ በአምስት እንጀራ አምስት ሺ ሰቦችን አጠገብኩ።

41. የውሃምንጭ እኔ ነኝ የተጠማ ይምጣና (ወደኔ) ይጠጣ የእውነት ፀሐይም እኔ ነኝ የኔ ፀሐይነት በአማንያን መሐይምናን ልብ ውስጥ ያበራል ፀሐይዋስ ወጥታ ትጠልቃለች ክርስቶስ ግን የማይጠፋ ፀሐይ ነው።

42. ደግሞም እንዲህ አለ መድሐኒትና ሕይወት እኔ ነኝ ልቡ የጨለመበትን ሰው የማበራለት እውነተኛ ፋና እኔ ነኝ ትእዛዜን

አልባቢሆሙ ከመኢይምዕኦሙ ዲያብሎስ እስመይሁብኦሙ ለመሐይምናን ከመኢይዕቀቡ ትእዛዝየ።

43. ወይቤ አነ ውእቱ ሕይወት ወዘየአምን ብየ እመኒ ሞተ የሐዩ ወአነ አነሥኦ በደሐሪት ዕለት ውስተትንሣኤክብር አንትሙኒ ዕቀቡ ትእዛዝየ ሊቃናት እለቤተክርስቲያን አዝዝዎሙ ከመ ኢይግበሩ ምግባረጽልመት እስመ ምግባረ ጽልመት ይመርሕ ውስተ ሞት ወሞትኒ ያወረድ ውስተ ሲኦል።

44. አንተኒ ኦ ወልድየ ቀሌሜንጦስ ዕቀብ ወንግሮሙ ለሕዝብ ከመይድኅኑ እምዝሙት እስመ ታረኩስ ነፍሰ ወሥጋ ሕቡረ ለአለ የሐውሩ ባቲ። በከመይቤ እሁነ ጳውሎስ ብእሲ ዘኀጢአተ ይገብር አፍአ ይኤብስ በሥጋሁ እስመ ለመሐይምናን እሞሙ ቅድስት ቤተክርስቲን ወአቡሆሙ እግዚአብሔር።

45. እስመነሳእነ ሥጋሁ ወደሞ ወበእንተዝ ኮነ አሐወ መፍትውኑ ከመይርኰሱ አሐው ምስለአሐቲሆሙ ወበእንተሰ ተዋስቦ ወተዋልዶ ዘርእ ትዋሰቡ በአሐዱ ኪዳን ወይ ንበር ብእሲ በአሐቲ ብእሲት ወበእንተዝ ከላእነ ዝሙተ።

47. ወበእንተዝ ፀልአ እግዚአብሔር ዝሙተ ወአዘዘነ ከመይፅንዑ ሕዝብ በቅድስት ቤተክርስቲን ወኢይኩኑ

የሚጠብቁ ሁሉ ልቡናቸው ይበራል ዲያብሎስ ትእዛዜን እንዳይጠብቁ ይፈታተናቸዋል።

43. እንዲህም አለ ህይወት እኔ ነኝ እኔን የሚያምን ቢሞትም እንኳ ይድናል እኔም በኋለኛዋ ዕለት በክብር አነሳዋለሁ እናንተም ትእዛዜን ጠብቁ እናንተ የቤተክርስቲያን አለቆች ትእዛዜን ጠብቁ የጨለማንም ሥራ እንዳይሠሩ ንገ አውጡአቸው የጨለማ ስራ ወደሞት ይመራል ሞትም ወደሲኦል ያወርዳል።

44. ልጄ ቀሌሜንጦስ ሆይ አንተም ጠብቅ ህዝብም ከዝሙት እንዲጠበቁ ንገራቸው ዝሙት ነፍስንና ሥጋን ያረክሳል ስለዚህም ወንድማችን ጳውሎስ በስተውጭ ሐጢአትን የሚሠራ ሰው በሥጋው ከፍተኛ በደልን ይፈፅማል ብሏል የመሐይምናን እናታቸው ቅድስት ቤተክርስቲያን ስትሆን አባታቸው እግዚአብሔር ነው

45. ሁላችን ክርስቲያኖች የክርስቶስ ሥጋና ደም ተቀብለናል ስለዚህ ሁላችን ወንድምና እህት ነን ይህ ሁኖ እያለ ወንድሞች ከእህቶች ጋር ሥጋቸውን ማርከስ ይገባልን ባንድ ቃልኪዳን በመሆን ለመጋባትና ለመዋለድ ሲባል ከዝሙት በራቀመንገድ መገባት ተፈቅዷል።

47. ስለዚህ እግዚአብሔር ዝሙትን ጠላ ህዝቦች በቅድስት ቤተክርስቲያን ብቻ እንዲፀኑ እንድናስተምራቸው አዞናል

ፈታውያነ ዝሙት እስመ ፍትወት ታወርዶ ለሰብእ ውስተ መሥገርተ ሠይጣን።

48. ወበፍትወተ መብልዕ ተሠግረ አቡነ አዳም ወወረደ ውስተዛቲ ምድር ርግምት እስመ ተረግመት ምድር ህየንተ አዳም ወበእንተዝ ወረደ እግዚአብሔር እምልዑል ማህደሩ ዲበምድር ወተሰብአ እማሪያም ቅድስት ድንግል ወኮነ ሰብአ ዘእንበለንጢአት ባሕቲታ ወተወልደ በቤተልሔም በከመ ሰበኩ ነቢያት።

49. እንሶሰወ ወአስተርአየ ሰበከ ወመሐረ ጥምቀተ ለሥርየተኀጢአት ወተጠምቀ በእደዮሐንስ ካህን ወእምድሕሬሁ ፈወሰ ድውያነ ወከሰተ አዕይንተዕውራን ወአሕይወ ሐንካሳነ ወአስምዐ ፅሙማነ ወአስተናገረ በሀማነ ወጌሠ ላእለባሕር ወሆረ ዲቤሃ ከመዘየሀውር ዲበየብስ

50. ወአንሥአ ለአልአዛር እመቃብር ወአሀየዎ ወሐመዩዎ አይሁድ እንዘይብሉ ይኄይስ ይሙት ፩ብእሲ እምይትሐጐል ኵሉ ሕዝብ ወዘንተ ተነበየ ሊቀካህናቲሆሙ ቀያፋ እንዘ ይብል ከመዝ እንዘይመስሎ ዘያሜክሮ ወካዕበ ይቤልዎ ወሐመዩዎ እምአይቴ ሎቱ ዛቲ ጥበብ አኮኑ ወልደዮሴፍ ፀራቢ።

ዝሙትን የሚወዱ እንዳይሆኑ እናስተምራቸው ፍቅረዝሙትና ፍቅረ መብል ወደሠይጣን ወጥመድ የሰውን ልጅ ታስገባለች።

48. በመብል ፍቅር አባታችን አዳም ከወጥመድ ገባ ወደተረገመችም ምድር እንዲወርድ ተደረገ ስለአዳም ምድር ተረግማለች ስለዚህም እግዚአብሔር ከልዑል መንበሩ ወደምድር ወረደ ከቅድስት ድንግል ማርያምም ስጋ ለብሶ ነቢያት እንደሰበኩት በቤተልሔም ተወለደ።

49. በምድር ተመላለሰ በግልፅም ታየ ጥምቀትንም ለሐጢአት ሥርየት አስተማረ በካህን ዮሐንስ እጅ ተጠመቀ ከዚያውም በኋላ በሽተኞችን ፈወሰ የዕውራንንም ዓይን አበራ አንካሳዎችንም አዳነ ለምፃሞችን ከለምፃቸው እንዲነፁ አደረገ መስማት የተሳናቸውንም እንዲሰሙ አደረገ ዲዳዎችን አናገረ ባሕርንም ዳሰሳትና ሰዎች በየብስ እንደሚጓዙ ተጓዘባት

50. አልአዛርን ከመቃብር አስነሳው ነገር ግን አይሁድ ብዙ ሕዝብ ከሚጠፋ አንድ ሰው ቢሞት ይሻላል እስከማለት አሙት ይህን የነሱ ሊቀካህናት የሆነው ቀያፋ ይህንን ትንቢት ተናገረው ቀያፋ ትንቢት እናገራለሁ በማለት የተናገረው ሳይሆን ጌታችንን ለመግደል ብሎ ነው በሁለተኛው መንገድ አይሁድ ይህ ጥበብ ከማን ተሠጠው የጠራቢው ዮሴፍ ልጅ አይደለምን በማለት አሙት።

1. እሙኒ ማርያም ዘእምነገደይሁዳ ንሕነሰ ዘእምሌዋውያን እሙንቱ ንሕነ ንገብር ግብረክህነት በውስተቅድስተ ቅዱሳን እስመ ነገደሌዊ ሐረየ እግዚአብሄር ለክህነት አው ለዝንቱ እምአይቴ ሎቱ ወበእንተ ሰንበትሂ ተገአዘዎ አይሁድ እንዘብሉ ዝ ብእሲ ኢኮነ እምእግዚአብሔር ዘኢያከብር ሰንበተ ወኢያከብር ሕገኦሪት ወእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ አስተቈጥዖሙ በገቢረ ግብሩ በዕለተሰንበት።

52. እመቀዳሚሃ ትቤ ቅድስት ኦሪት ፈጺሞ ኲሎ ገቢረ ግብሩ አዕረፈ በዕለተሰንበት ዘውእቱ ሳብዕ ዕለት ወሶበመዕአ ሠራዒሃ ለሰንበት ህየንተ ዘኢገብረ ቀዳሚ ፈደየ ዕዳሃ ወገብረ ላቲ ግብራ እስከ ይትቈጥዑ አይሁድ በሕቀ በምዕአቱ ኀቤነ ገብረ ዕቡረ ወአሕየወ ዕውረ።

53. በሰንበት ለመፃጕዕ ዘ፴ወ፰ ክረምተ ሐመ አሕየዎ ወለአሐተ ብእሲት እንተ አድወያ ጋኔን አሕየዋ በሰንበት ለወለተኢያኤሮስሂ አሕየዋ በሰንበት ኲሎ ዘገብረ ተአምረ ወመንክረ በሰንበት

54. ኲሎ ተአምራተ ወመንክራተ በሰንበት ገብረ ከመያግብአነ ውስተግብር ዘበአማን በእንተዘገብረ ባቲ በቀዳሚ መዋዕል አመፈጠረ ሰማየ ወምድረ ወሶበ ተገአዝዎ አይሁድ በእንተ ሰንበት ውእቱ ይቤሎሙ አቡየሂ ይገብር ምሕረተ

51. እናቱ ከይሁዳ ነገድ የሆነች ማርያም ናት እኛ ግን ሌዋውያን ነን ስለዚህ ላበታችን ሌዊ ክህነት ከእግዚአብሔር ተሠጥቷል እኛም ወደቅድስተቅድሳት እየገባን ግብረክህነትን እንፈፅማለን ስለዚህ ሰው ክህነት ከማን ወገን ተሠጠው አሉ ስለሰንበትም ብዙ ክርክር አነሱበት እንዲህም አሉ "ይህ ሰው ከእግዚአብሔር የተላከ አይደለም በመሆኑም ሰንበትን አያከብርም ህገኦሪትንም አይጠብቅም" አሉ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ግን በሰንበት ሥራውን እየሠራ ያስቆጣቸው ነበር።

52. ቅድስት ኦሪት እግዚአብሔር ሥራውን ሁሉ ፈፅሞ በዕለተሰንበት ዕረፈ ትላለች ይህም ሰባተኛው ዕለት ነው ሰንበትን ይሠራ በመጣጊዜ ግን ዕዳዋን ከፍሏል ሥራዋንም ትሠራለች በዚችው ዕለት ሥራውን ሠራ በዚሁም አይሁድ ጌታችን ከመጣ ጀምሮ በጭቃ ዓይነሥውሩን አዳነ

53. በሰንበት ዕውርን አዳነ ሰላሳስምንት ዓመት የታመመውንም በዕለተሰንበት አዳነው ጋኔን አድርባት የታመመችውንም ሴት በእለተ ሰንበት አድኗታል። የኢያኤሮስንም ሴት ልጅ በዕለተሰንበት ከታመመችበት በሽታ አድኗታል።

54. ብዙ ተአምራትን መንክራትን በሰንበት አድርጓል ይህንንም በዕለተ ሰንበት ሥራን መሥራት (መልካም ሥራን መሥራት) እንደሚቻል አረጋገጠ። በመጀመርያ ሰማይንና ምድርን ሲፈጥር ሰንበትን ከፍ አድርጓታል አይሁድ ስለሰንበት በተከራከሩት ጊዜ

በሰንበት ወእነሂ እገብር ለአቡየ ወበእንተዝ ገብረ ገብሮ በዕለተሰንበት ወእሙንቱሂ ተቆጥዕዎ ፋድፋደ ወወሀብዎ ያግብእ ሴጠ ለክቡር ብሩረ ወእምዝ አሐዝዎ።

55. ወእምዝ አሐዝዎ በከመይቤ በወንጌል ወሰቀልዎ በእንተ ኃጢአትነ ወተንሥአ በሣልስት ዕለት ወመሐረነ ሕጎ ወሥርዓቶ እስመነበረ ምስሌነ ፵ መዓልተ ወሌሊተ።

56. ወከማሁ መሐረነ እግዚእነ እንዘይብል ዕቀቡ ሥርዓትየ ዘመሐርኩክሙ ወአለበውኩክሙ አለብውዎሙ ለአብዳን ወአስተፍስሕዎሙ ለትኩዛን ወአዕድቅዎሙ ለሐጥአን ወወሀብዎሙ ንስሐ ለውዱቃን ወናዝዝዎሙ ለሕዙናን ወሚጥዎሙ ለአረማውያን ውስተ ክርስትና።

57. ወኢታስትቱ ትእዛዛተሕግ ዘሠራዕኩ ለክሙ እስመእሄሉ ምስሌክሙ እስከ ሕልቀተ ዓለም ወአረትኣ ለቃልየ ወለቃልክሙ ላዕለኩሉ ዘይሰምዕ ትእዛዝየ ወዘሰ ኢሰሐቦ አቡየ ኢይክል መጺአ ኀቤየ እስመቦ ዘየሐውር ሰሚያ ውስተ ሕይወት ኢሰምአ ቃለመለኮት ዘሰበክሙ አንትሙ። ወእመቦ ዘየዓልዎ ለቃልክሙ ወይወርድ ውስተኩነኔ ደይን ኀበ አልቦ ወጺአ እስከ ለዓለመ ዓለም።

58. ዕቀቡ ሕግየ ወኢታስትቱ እምሥርዓትየ ዘሠራዕኩ ለክሙ

እሱም እንዲህ አላቸው "አባቴም ምሕረትን ያደርጋል። እኔም የአባቴን ሥራ እሠራለሁ" በዚህ ጊዜ አይሁድ እጅግ ተቆጡት በዚሁም ክቡሩን አምላክ በገንዘብ አሳልፈው ሸጡት።

55. በወንጌል እንደተፃፈው አይሁድ ያዙት ስለኛም ሐጢአት ተሰቀለ በ3ኛው ዕለትም ተነሳ ሥርዓቱንና ህጉንም አስተማረን ከዚያ በኋላ ፵መዓልትና ፵ሌሊት ከኛ ጋር ኖረ።

56. ጌታችን እንዲህ ሲልአስተምሮናል ሥርዓቱን ጠብቁ አስተምሬአችሁ አለሁና ልብ ብላችሁም እንድትረዱት አእምሮአችሁ ከፍየላችሁ አለሁና ሰነፎችን ልባሞች አድርጉዋቸው ያዘኑትንም አስደስቱ ሐጢአተኞችን አፅድቁ የወደቁትን በንሥሐ መልሱ። ያዘኑትንም አስደስቱ ሐጢአተኞችን አፅድቁ የወደቁትን በንሥሐ መልሱ ያዘኑትን አጽናኑ አረማውያንን አስተምራችሁ ወደክርስትና መልሱ።

57. እኔ የሠራሁላችሁን ህግ ትእዛዝ አታቃልሉ እኔ እስከዓለም መጨረሻ አልለያችሁም ቃሌንም በሚሰማችሁና በሚከተላችሁ ሁሉ አኖራለሁ አባቴ ያልሳበው ወደኔ ሊመጣ አይችልም የሕይወትን ቃል ሰምቶ የሚሄድ ይኖራል እናንተ የምትሰብኩት የመለኮት ቃልነው። የናንተን ቃል የማይቀበል ካለ ወደሲኦል ይወርዳል።

58. ሕጌን ጠብቁ ከሥርአቴ የምታቃልሉት አይኑር በቅድስት ድንኳን

በቅድስት ደብተራ ኀበእትናገር በውስቴታ
ውስተአልባቢክሙ እስመምሥአል ወምሥትሥራየ
ኀቢአት ይእቲ።

59. እስመ ዕፁብ ታቀልል ወትረድእ ለዘተመንደበ እስመ
መፍቀሪተ ነግድ ይእቲ። ወለዘሰአለ ትሁብ ምሕረተ
እስመ ማሕደረ ትፍሥሕት ይእቲ።

60. ወእለይትመረኰዝዋ ኢይተነትኑ ለዓለም እስመ ፅኑዕ
መሠረተድዳ በኀይለመስቀሉ ለኢየሱስ ክርስቶስ ዘአድኀና
በደሙ ወአተባ በዕፀ መስቀሉ ከመትኩን ምስትስራየ
ኀጢአት።

61. ኦ ወልድየ ቀሌሚንጦስ ዘንተ ሥርዓተ ዕማሪቅበሙ
ለሥዩማነቤተ ክደርስቲያን ከመይዕቀቡ ሥርዓተ ቅዱሰ
እምኀበ እግዚአብሔር ዘተሠርዓ በደብተራጽድቅ
በኢየሩሳሌም እንተ በውስቴታ በላዕሉ ይሴብሑ መላእክት
ወኵሎሙ ትጉኃን ኃይለሰማያት ወ፼ አእላፋት
ወትእልፊተ አእላፋት ወማሕበረ በኵር እለፅሑፍ
አስማቲሆሙ ውስተ መፅሐፈ ሕይወት በኢየሩሳሌም
ሰማያዊት እንተ በሰማያት።

62. ወይእተ ታበፅሖሙ ኀበእግዚአብሔር ለዕጉሳን እለ ይነብሩ
ውስቴታ ወትቤሎሙ ነዑሙ ውሉድየ እለ ይተግሁ ኀቤከ
መዓልተ ወሌሊተ በውስቴትየ ወየዐቅቡ ሥርዓትየ

አድሬ እናንተን የማፅናናበትን ኃይሌ ሠርቻለሁ እሷ መሃፀኛና
የሐጢአት ሥርየትን መሥጫ ናት

58. እሷ ጭንቅን ታቃልላለች የተቸገረውንም ትረዳለች እሷ እንግዳን
የምትወድ ናት ለለመነ ይቅርታን ታሠጣለች የደስታ ማደርያ
ናትና

60. እሷን የሚመረኰዙ አይፍገመገሙም መሠረቷ የፀና ነውና
የፀናውም በኢየሱስ ክርስቶስመስቀል ነው እሱ በደሙ
አድኗታልና በዕፀመስቀሉም ባርኳታልና የሐጢአትማስተሠርያ
ትሆን ዘንድ

61. ልጄ ቀሌሚንጦስ ሆይ የሠጠሁህን ሥርዓት ለቤተክርስቲያን
ሹማምንት በአደራነት አስረክባቸው እነሱም በዚሁ እየተመሩ
ቅዱሱን የእግዚአብሔር ሥርዓት ይጠብቁ ይህሥርዓት
በእውነተኛው ድንኳን ተሠርቷል እቺም ድንኳን በሰማያዊቷ
ኢየሩሳሌም ትመሰላለች ሰማያዊቷ ኢየሩሳሌም አእላፋት አእላፈ
አእላፋት መላእክት ኃይላትም ማሕበረ በኵር በሚባል
የሚታወቁትም ሁሉ ለአምላክ ተገዢነታቸው የሚገልፁባት ናት
የሁሉም ስም በሰማያዊቷ ኢየሩሳሌም ተፅፏል።

62. እቺ ሥርዓት ወደእግዚአብሔር ታደርሳቸዋለች ትዕግሥተኞች
በውስጧ ስለሚኖሩ ልጆቼ ትላቸዋለች እነዚህ ትዕግሥተኞች
በተቀደሰው ትጋታቸው ሌትተቀን እግዚአብሔርን ለማገልገል

ለገዘሉፉ በእንተ ሥርዓት ዘሠራዕኩ ሎሙ ወታወርሶሙ መንግሥተ ሰማያት ዘመሐለ ለአበዊሆሙ ለእለ ተአመንዎ።

63. ኦ ወልድየ ቀሌሚንጦስ ዕቀብ ሥርዓተ ሕሩየ ዘተወፈይከ እምኀበእግዚአብሔር ውስተ እዴከ እስመ አነ ተወፈይኩ እምኀቤየ መራትተ መንግሥተ ሰማያት አንተኒ ትኅሥእ እምኀቤየ ዕቀብ ወአወፍዮሙ ለሊቃውንተ ቤተክርስቲያን እለሐለው እምታሕቴከ አማሕፅኖሙ ይዕቀቡ ሥርዓታ ለቅድስት ቤተክርስቲያን።

64. ወእሙንቱሂ ይሥርዑ ዘከመ ክህሉ ለዲያቆናት ወንፍቀ ዲያቆናት ወለሕዝብ ለእድ ወለአንስት ወለሕፃናት አዝዝዎሙ ከመያርትዑ ሐዊረ በፍኖተ ጽድቅ ዘሐዋርያት ዘሠርዑ ለቤተክርስቲያን ዘከመ አዘዝነ ቀዳሚ ውስተ ሕግነ ወንቤ ኩሎሙ እለቤተክስቲያን በውስተ ምቅዋሞሙ ለሊቃነ ጳጳሳት ወሊቃነ ካህናት ቀሳውስት ወዲያቆናት ወአናጉንስጢስ

65. ወለሕዝባውያን አእሩግ ወሕፃት ወአንስት ቅዱሳት ወደናግል ወመዓስብ ዕቤራት ወዕጓለማውታ ወዲያቆናዊት እለየዓቅቡ አብያተ መበለታት ፍሉጥ ምቅዋሞን በበይናቲሆን።

ይተጋሉ እነሱ እናንተ በምትሠጡዋቸው ሥርዓት ይመራሉ። በቅድስት ቤክርስቲያን አማካይነትም መንግሥተ ሰማያትን ይወርሳሉ ለአባቶቻቸው ምሎላቸዋልና

63. ልጄ ቀላሚንጦስ ሆይ የተመረጠውን ሥርዓት ጠብቅ ይህም ከእግዚአብሔር በእጅህ የተቀበልከው ነው እኔ የመንግሥተሰማያትን ቁልፍ ተረክቤአለሁ አንተም ይህንኑ ከኔ ትረከባለህ ይህንኑን አንተም ጠብቀህ ካንተ በኋላ ለሚነሱ የቤተክርስቲያን አስተባባሪዎች አስረክባቸው እነዚህም አንተ የበታቾችህን አድርገህ የምትሾማቸው ናቸው የቤተክርስቲያንን ሥርዓት ይጠብቁ ዘንድ አደራ በላቸው።

64. እነሱም እንደሚገባ አድርገው ሕግን ይሥሩ ሕጉም ለዲያቆናት ለንፍቀዲያቆናት ለሕዝብ ለወንድና ለሴቶች ለሕፃናት የሚስማማ ይሁን እነሱም በእውነት መንገድ ይራመዱ። ሐዋርያት ለቤተክርስቲያን ሥርዓትን ሠሩ። ይህም እኛ ባዘዝነው መሠረት የተሰራ ነው ይህ ሥርዓት ይወጣ ዘንድ አስቀድመን አዘናል ባወጣነውም ህግ መሠረት የጳጳሳት የካህናት አለቆች የቀሳውስት የዲያቆናትና የአናጉንስጢስ የመቆምያ ቦታ ወስነናል።

65. እንዲሁም ለሕዝባውን ለሽማግሌዎች ለሕፃናትና ለተመሰገኑ ሴቶች ለደናግል ለመዓስባን ባልቴቶችን የሙት ልጆችን ዲያቆናዊቷን ሌሎችም ቤክተርስቲያንን የሚጠብቁትን መቆምያቸው እየራሳቸው እንዲሆኑ ይገባል

66. ይዑዱ አብያተ ክርስቲያናውያን ወውስተ ኵሉ አብያተአንስት ወይዑዱ ዲያቆናት ውስተ ኵሉ አብያተ ምዕመናን ከመ ኢይትሀከዩ ሠርከ ወነግሀ ገነየ ወገይሰ ውስተ ቤተክርስቲያን እንዘ የአኵትዎ ለእግዚአብሔር ሠርከ ዘወንበነ እግዚአብሔር ብርሃነ ዕለት ለተግባረ ሰብእ በዘየሐዩ ወይረድኦ ለፅኑዕ።

67. ወዘነግሀ የአኵትዎ እንዘይብሉ በእንተ ዘሐለፈ እምኔሆሙ ጽልመተ ሌሊት ወአዲ በእንተ ዘወሀቦሙ ዕረፍተ ፃማ ኀሐ ፅባሕ ትትሜሰል ለትንሣኤ ሙታን ወንዋመ ሌሊት ትትሜሰል በሞት።

68. ወበእንተዝ ይጊሱ ሠርከ ወነግሀ ውስተቤተክርስቲያን አዘዝነ በቀኖና ከመኢያስትቱ ክርስቲያን ገይሰ ቤተክደርስቲያን ሠርከ ወነግሃ ቀትረ ወሰዓተ ወይጼልዩ ሎሙኒ ወለቢጾሙኒ ለንጉሥኒ ወለበሓውርትኒ ወለኵሉ አዕዋፍኒ ለእንስሳትኒ ወለኵሉ ፍጥረት ዘፈጠረ እግዚአብሔር

69. ዘንተኬ ትእዛዘ ከመይጸልዩ ሎሙኒ ወለቢያሙኒ ወይጊሱ ቤተክደርስቲያን ሠርከ ወነግሃ በአንዱ ሕሲና እንዘይትፋቀሩ ምስለ ቢያሙ ወያቴሕቱ ርእሶሙ ወኢይስምዑ ውዴተ ላእለ ቢያሙ።

66. ዲያቆናት የክርስቲያኖችን የመኖሪያ ቤት ወዳለበት ሁሉ እየዞሩ የተቸገሩትን ሁሉ ይጎብኙ ችግራቸውንም ይመልከቱ ጥዋትም ሆነ ማታ ምእመናኑ በስንፍና እንዳይያዙ ለመንፈሳዊ አገልግሎት እንዲተጉ ያነቃቁዋቸዋል። በሠርክ በጧትና በማታም ወደቤተክርስቲያን ሁልጊዜ እየሄዱ ያመስግኑት እግዚአብሔር የዕለት ብርሃን ነው ሁሉንም ይረዳል

67. በንጋት እግዚአብሔርን ያመስግኑት የሌሊቱን ጨለማ ስላሳለፈ ዕረፍትንም ስለሠጣቸው ንጋት በትንሣኤሙታን ትመስላለች እንቅልፍ ደግሞ በሞት ትመሰላለች

68. ስለዚህ ክርስቲያን ጧት ማታ ወደቤተክርስቲያን ይገሰግሱ ዘንድ በቀኖና አዘናል ክርስቲያን ጧት ማታ ቀንና በየሰዓቱ ወደቤተክርስቲያን መገሥገሥን እንዳያቋርጡ ስለራሳቸውና ስለሹማምንት፣ ስለባልንጀሮቻቸው፣ ስለባሕር፣ ስለወፎች፣ ስለእንስሳትና እግዚአብሔር ስለፈጠራቸው ፍጥረታት ሁሉ በትጋት ያለስንፍና በአንቀዕድዎ ያለቸልተኝነት እንዲፀልዩ አዘናል

69. ይህን ትእዛዝ የተሠጠው ክርስቲያኖች ስለራሳቸውና ስለባልንጀሮቻቸው እንዲጸልዩ ነው ጧትና ማታ ወደቤተክርስቲያን ሲሄዱም ባንድልብ ባንድ ሐሳብ በመሆን ፍቅርን በማፅናት ነው ትሕትናም ይኑራቸው የስብቀት ነገርንም አይስሙ

70. ሶቤሃኒ ይተግህ ወይብል አበስኩ ሥረይ ሊተ ከመዝ ይኩን ምግባርሙ ለክርስያቲን እመኒ ተምዕዕዎ ይብል ሥረይ ሊተ ወያትሕት ርእሶ ከመ ዘአበሰ እንዘ ይኤብሱ ላእሌሁ ከመ ዝኬ ትትዓወቅ ግብረ እግዚእነ ኢየሱስ ክደርስቶስ::

71. ውእቱ ፈፀመ ሕጋ ለቤተክርስቲያን ወንሕነኒ ዘንተ ሠራዕነ ለክርስቲያን መሐይምናን እለ ተወከሉ በእግዚአብሔር ወበቅድስት ቤተክርስቲያን ከመ የሀበሙ አስበ ስብሐቶሙ::

72. ወዘተዓገሠ ሕማመ ወምንዳቤ ዲበምድር ከመይርከብ ተስፋ ዘበሰማት ኀበኢይበለኒ ፀኢይማስን ሰራዕነ ቀናና ለቤተክርስቲያን

73. እስመዘተሀየለ ላእለቢጹ ወተአገለ ንዋዩ በዓመፃ አው ክህደ ምዕቅብናሁ አዝዝዎ ከመ የሀበ ምክብኢተ ህየንተ ዘዓመጸ ኢይኩን ተአጋሴ ወኢይትአገል ንዋየቢፁ::

74. እስመ እዙዝ እማህበራ ለቅድስት ቤተክርስቲን ከመ ኢያዕቢ ርእሶ ክርስቲያን ላእለቢፁ ወያስተፍስሖሙ ለትኩዛን ወይናዝዞሙ ለሕዙናን ከመይግበር ፍትሀ ወሰላመ ማእከሌሆሙ ወይርዳእ ፅኑሳነ ወአከ ዘየሐይድ ንዋየ ቢፁ በዓመፃ::

70. ክርስቲያን በራሱ ላይ በደል ቢደርስበትም አጥፍቼአለሁ ይቅርበሉኝ ይበል ይህ አካሄድ በክርስቲያኖች የተለመደ መሆን አለበት ሰዎች በሱ ላይ ዘለፋ ቢያሰሙ እንኳ እንደበደለ ሁኖ ይቅርታን ይጠይቅ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በግብር ይህንን አስተምሮናል

71. እሱ የቤተክርስቲያንን ህግ ፈፅሟል እኛም እሱን መሠረት አድርገን የቤተ ክርስቲያንን ህግ ሠርተናል ህጉም እግዚአብሔርን አምነው በቅድስት ቤተክርስቲን የድካማቸውን ዋጋ ይሠጣቸው ዘንድ ይህን ሠርተናል

72. በሰማያት ተስፋ ያገኝ ዘንድ በዚህ ዓለም ሕመምንና ችግርን የሚታገሥ ስለሱ የቤተክርስቲያንን ቀኖና ሠርተናል::

73. በባለእንጀራው ላይ በደል የፈፀመ ካለ የባለንጀራውንም ገንዘብ የቀማ ካለ ወይም አልወሰድኩም ብሎ ከካደ በአደራነት የተቀበለውንም የካደ ቢኖር ለባለንብረቱ ዕጥፍ አድርጎ ይክፈል ማንም ክርስቲያን ግን በዚሁ መገኘት የለበትም

74. በቅድስት ቤተክርስቲያን ማሕበር የታዘዘው ክርስቲያን ራሱን ከፍ እንዳያደርግ ነው በባለንጀራው ላይ እንዳይታበይ የተከዙትን እንዲያስደስታቸው ሐዘንተኞችን እንዲያፅናናቸው ሰላምንና ፍትህን በመካከላቸው እንዲያሰፍን የተቸገሩትን እንዲረዳ በዐመፁ የባለንጀራውን ንብረት የማይቀማ ይሁን

75. ዘንተ አገዘዞሙ ለእለእምታሕቴክ ወእምሥልጣንክ እለየሐውሩ ውስተቅድስት እንተላእለኩሉ ቤተክደርስቲያን ሐውፆሙ ወአሰንዮሙ ወኢትመንን እንተ ደወየት በእንተ እግዚእክ ወዘልገሠት ወለእመ ተሰብረት እደዊሃ ወእገሪሃ እሥር ከመኢታሕጉል መሐስአ እግዚእክ።

76. ወፁራ ዲበ መታክፍቲክ ወአብኣ ውስተ ቤተ እግዚእክ ውስተዐፀደ ጸዴ ዘሕያዋን ወእምዝ ርኢ ኀበቈስለት ወህፅባ ወብጥሓ ወሱጥ ውስቴቱ ዜወ ወወይነ እስመኵሉ በዜው ይትመላሕ ከመትሕየው ለክ ዝልግሥት በግዕት እስመ ኢተአምር ኀበ ሐይወት ዘትገብር ለክ ፍሬ ለመዝገበ እግዚእክ ዘይተ ወወይነ ወሥርናየ።

77. ወሶበ ትሠርህ በአምልኮ ጣፆት ህፅባ ወአንፅሓ እምንጢአት ወአሠንያ በንሥሐ ከመ ትኩን ንፅሕተ ለመዝገበ እግዚአብሔር እግዚእክ። እመሂ በክህደት ወእመሂ በእምነት እመሂ በፆም በዘኮነ ግብር አሠኒ ወአስተሐምም ለፈውሶታ ከመትኩን ንፅሕተ ወትትወደይ ውስተ መዝገበ እግዚእክ ወኢይኩን ክርዳደ ዘያውዕይዎ በእሳት

78. ክርዳድሰ ሐጥእ ውእቱ ዘኢይትመየጥ ውስተንሥሐ

75. ካንተ በታች ላሉ የቤተክርስቲያን ሹማምንት ይህን እንዲፈፅሙ እዘዛቸው። ከሁሉ በላይ ወደሆነችው ቅድስት ቤተክርስቲያን ለሚሄዱ ሁሉ ጎብኛቸው ደስም አሰኛቸው የታመመች በግም ብትኖር አትናቃት እጅና እግሮቿም ቢሠበሩ አሥረህ እንድትጠገን አድርግ የጌታህን ግልገል አታጥፋ.

76. የታመመችውን በግ በትከሻዎችህ ተሸክመህ በመውሰድ ወደጌታህ ቤት አድርሳት ከጤናማ በጎችም ለመጨመር ህክምና አድርግላት የቆሰለውን አካልዋ በወይንና በጨው እጠበው የሚያስፈልገውም ከሆነ ብጣው እንደገናም ጨውንና ወይን በቁስሉ ላይ አፍሥስበት በጨውና በወይን በሽታ ሁሉ ይነቀላል። እቺ የታመመች በግ ስትድን ለጌታህ መዝገብ የምታስገባውን ፍሬ አታውቅም

77. የሰው ሕይወት ጣዖትን በማምለክ ብትደክም ከሐጢአት አንፃት በንሥሐም አካሄድዋን እንድታስተካክል አድርግ ለጌታህ እግዚአብሔር መዝገብ ንፁሕ ሥንዴ ሁና እንድትቀርብ በክሕደት ይሁን በእምነት በፆም ይሁን በጸሎት በማንኛውም ሁኔታ ብትገኝ በተሠጠህ ሐላፊነት ከእግዚአብሔር ጋር ያላትን ግንኙነት እንድታስተካክል አድርግ ከነፍስ ሕመም ፈውሳት በዚህ ጊዜ ንፁሕ ስንዴ ሁና ወደጌታ መዝገብ ትገባለች እንክርዳድ ሁና ወደእሳት አትጣልም

78. እንክርዳድ ማለት በንሥሐ ወደቅድስት ቤተክርስቲያን

ውስተ ሥርዓታ ለቅድስት ቤተክርስቲያን እንተአነ እንተተዓቅብ ሥርዓታ በኩሉ ጊዜ ወአንተሰ አዝዞሙ ለሊቃውንተ ቤተክርስቲያን እሙንቱኒ የአዝዝዎሙ ለሊቃውንተ ሕዝብ ለነገሥት ወለመኳንንት እንበለፍርሐት በእንተ ሥርዓታ ለቅድስት ቤተክርስቲያን

79. መዓድዎሙ ወአለብውዎሙ ዘተሠርዓ ሎሙ በሕግ ወአንተኒ መኮንን ለእመኮንከ በከመ ዕበይከ ስማዕ ቃለ እግዚአብሔር ዘነገሩከ ቃለ ሊቃውንተ ቤተክርስቲያን ወኢትፍርሖሙ ወኢትኅዝን ላእሌሆሙ በትዕቢት ወበትዝሕርት ከመ ኢይትመዓዕከ እግዚአብሔር ወኢታንብር ቂመ ውስተ ልብከ በእንተ ዘነገሩከ ቃለእግዚአብሔር በእንተ መድኀኒተ ነፍስከ።

80. ወእመኒ ንጉሥ አንተ በከመትቤ መንግሥትከ አፍቅር ቃለ እግዚአብሔር ከመይንግሩከ ወኢትትዓወሮሙ ለእለ ነገሩከ አላ አፍቅሮሙ ፌድፋደ ከመ ነፍስከ ወኢትትገረም ላእሌሆሙ ከመ ኢይትመዓዕከ እግዚአብሔር በመዓቱ።

81. ወካዕበ ፍርሐ ለዘይኴንን ነፍሰ ወሥጋ ሕቡረ ወኢታእትት ቃሎሙ ዘነገሩከ እስመ ዘይትዔወር ቃለ እግዚአብሔር የሐፅፅ መዋዕሊሁ ወያገብእ ላእሌሁ ኵሉ እኩየ ዘነበበ

የማይመለስና በሷ እየተመራ የእግዚአብሔር ቤተሰብ ለመሆን የማይፈልግ ማለት ነው። አንተ ግን የቤተክርስቲያንን ዐለቆች የሕዝብን አለቆች ይመክሩዋቸውና የእግዚአብሔርን አካሄድ ለሕዝብ ያስተምሩ ዘንድ እዘዛቸው የሕዝብ አለቆቹም ሳይፈሩ በጥብአት ነገሥታቱንና መኳንንቱም ያስተምሩ

79. በህግ የተሠራላቸውን ምዕመናን ይከተሉ ዘንድ ንገሩዋቸው አስረዱዋቸውም አንተም ልትሠማው የሚገባህን የእግዚአብሔር ቃል ከመስማት ወደኋላ አትበል። የቤተክርስቲያን መሪዎች የሚሠጡህን ትምህርት በትሕትና ተቀበል ሰውን አትፍራ ትዕቢትና ትዝሕርት አይደርብሕ እግዚአብሔር እንዳይቆጣህ ቂምን በልቡናህ አትያዝ ነፍህን ለማዳን ከመምህራን ስለሚደርስብህ ተግሣፅ ቅሬታ አይኑርህ።

80. አንተ ንጉሥ ብትሆን ባለህ የመንግሥት ሥልጣን ልክ ቃለእግዚአብሔርን ውደድ ይህ ከሆነ ነው መምህራን የሚነግሩህን ልትረዳ ምትችለው ሥልጣን አለኝ ብለህ መምህራንን ችላ አትበላቸው እንደነፍስህ ውደዳቸው እንጂ። በምድራዊ ሥልጣንህም አትክበዳቸው እግዚአብሔር በመዓቱ እንዳይቆጣህ።

81. ነፍስንና ሥጋን አንድ ላይ የሚኰንነውን ፍራው ከመምህራን የተነገረህን ቃለእግዚአብሔር አታርቅ ቃለእግዚአብሔርን ችላ የሚል ሁሉ ዕድሜው አጭር ይሆናል እግዚአብሔርም

ላእለሳኦል ወአከአብ ወኦዝያን።

82. በውእቱ መዋዕል እለተአደው ወተዐወሩ ቃለእግዚአብሔር እንዘ ነገሥት እሙንቱ ወኢያሰነዩ ምግባሮሙ ለዘይሬዕዩዎሙ ወኢያንበሩ በርትዕ እለ እምታሕቴሆሙ አበግዓ መርዔቱ ለእግዚአብሔር እለ አእቀቦሙ ከመ ይርአዩዎሙ በንፁሕ።

83. ወእመሰ አሕጉሉ እምዘ አዕቀቦሙ ሀሎ ዘይትሐሰሰሙ እግዚአብሔር ለእመ አጥፍኡ ነፍሳተ በከንቱ ነፍሳትሰ እለይርኅቁ ጳጳሳት እለቤተክርስቲያን።

84. አንተሰ ኦ ንጉሥ ትሬኢ ሥጋ ወጀከሙ ዑቁ ከመኢይታሕጉሉ መርዔቶ ለእግዚአብሔር።

85. አንተሂ ንጉሥ እነዘተኤስዮሙ አድኅኖሙ እምእለ ይትኤገልዎሙ እቡያን እለኢአቀቡ ፍትሐ ወይትዔበዩ በፅንዓኃይሎሙ።

86. ወአንተሰ አድኅኖሙ እምእደ ሐጥአን ወለእቤራት ወእጓለማውታ ለሥዑማን ወለሊቃነ ጳጳሳት ወእጓለማታ ለሥዑማን ወለሊቃነ ጳጳሳት ወእጓለማውታ ወለሥዑማንሂ ወለሊቃነጳጳሳት ይዕቀቡ ነፍሶሙ ከመ ኢይማአሙ

የገዛራሱን መጥፎ ንግግር በአክአብ በሳኦልና በኦዝያን ላይ እንደፈፀመው ሁሉ ያደርግበታል።

82. እነሳኦል ከእግዚአብሔር የተሠጣቸውን ሥልጣነ መንግሥት እንደገል ሥልጣን በመቁጠር ቃለእግዚአብሔርን ችላ አሉ ምግባራቸውን አላሳመሩም ከፍ ያረጋቸውን እግዚአብሔርን ችላ አሉ ምግባራቸውን አላሳመሩም ከፍ ያደረጋቸውን እግዚአብሔር ራሱ የበታቾቻቸውን በቅንነት አልመሩም እግዚአብሔር ግን አደራነትን ሠጥቶአቸው ነበር።

83. በአደራነት የተሠጡዋቸውን የእግዚአብሔር መንጋዎች ካጠፉ በሐላፊነት እግዚአብሔር ይጠይቃቸዋል። ነፍሳትንም በከንቱ ካጠፉ ዕዳቸው ብዙ ነው በዋነኛነት ነፍሳትን የመጠበቅ ሐላፊነት ያላቸው ግን ጳጳሳት ናቸው

84. ንጉሥ ሆይ አንተ ሥጋዊውን ሥራ ትጠብቃለህ ስለዚህ አንተና ጳጳሱ የእግዚአብሔር በጎች እንዳይጠፉ ተግታችሁ ጸልዩ

85. አንተ ንጉሥ ከመልካም አያያዝ ጋር ሰዎችን ከሚታገሉዋቸውና ፍርድን ከማይጠብቁ ትዕቢተኞች በፅናታቸውም ከሚታበዩ አድናቸው።

86. ንጉሥሆይ ከበደለኞችና ከሐጢአተኞች እጅ ባልቴቶችንና የሙትልጆችን አድናቸው። ከሊቃነጳጳሳት ጀምሮ ያሉ በውስጣቸው ያሉትን ሙት ልጆች ያስተዳድሩ ዘንድ ድጋፍን አድርግላቸው። ለሠይጣን እንዳይሸነፉም አበረታታቸው። ጳጳስ

ሰይጣን፡፡ ወአሠነዮሙ በንሥሐ ወአድኅኖሙ እምፀብኡ ለዲብሎስ ከመይትፌሳሕ እግዚአብሔር፡፡ በምሕሮቶሙ ወበዓቂበ መርዔቶሙ፡፡

87. ወዕቀቡ መርዔተክሙ እንዘተሰምዑ ዘንተ ቃለ ወኢታስትቱ ዘአመገበክሙ እግዚአብሔር በመግቦቱ በከመኢይትሐሰስ እግዚአብሔር እምኔክሙ በእንተ ዘኢመሐርክሙ ወኢገሠፅክሙ ለእለኢይሰምዑ እምኔክሙ፡፡

88. ወለእለሰምዑ ኢትፌንውዎሙ ውስተ ቤተ አበዊሆሙ ሕረማውያን ከመ ኢያማስኑ ሃይማኖቶሙ ወተመይጠቶሙ፡፡ አላ አፅንዕዎሙ እስከ ትፀንዕ ሃይማኖቶሙ ወኢትፌንውዎሙ ውስተ ክህደት ከመ ኢያክብዱ አልባቢሆሙ አበዊሆሙ ወአዝማዲሆሙ፡፡

89. እስመ አመ ትፌንዎ ለዘአምነ ወተመይጠ እምክህደት ውስተ ብሔረ አበዊሁ አላውያን ወከሐድያን ትብእስ ክሕደቱ እምዘቀዳሚ፡፡

90. በከመ ይቤ በወንጌል ኢተሀቡ ቅድሳተ ለከለባት ወኢትደዩ ባሕርየክሙ ቅድመ አሕርው ከመኢይኪድዎ በእገሪሆሙ ኢትስድድዎሙ ለእለአእመንክሙ ውስተ ግብረ

ሆይ ከዲያብሎስ ጠብ ምዕመናንን አድናቸው በዚህ እግዚአብሔር ደስ ይለዋል እግዚአብሔር መንጋዎቻቸውን ስለጠበቁ ደስ ይለዋል፡፡

87. መንጋዎቻችሁን ጠብቁ ይህንንም ቃል እየሰማችሁ ለመጠበቅ ትጉ፡፡ የእግዚአብሔርን መግቦት ችላ አትበሉ እናንተንም የሚመግብ እሱ ነውና መጋቢነታችሁም ችላ አትበሉ፡፡ ይህንን ባታደርጉ እግዚአብሔር በኃላፊነት ይጠይቃችኋል ባለማስተማራችሁና ባለመገሠፃችሁ የሚሰሙአችሁንም ባለማስተማራችሁ ይበቀላችኋል፡፡

88. ትምህርታችሁን ሰምተው ያመኑትን መልሳችሁ ወደቤታቸው አትላኩዋቸው ወደአረማውያን ቤተሰቦቻቸውም አይጨመሩ ሃይማኖታቸውን እንዳያጠፉ ሃይማኖታቸው እስክትፀና ድረስ በቅርብ እየተከታተላችሁ አፅኑዋቸው እንጂ በፍጥነት ወደዘመዶቻቸው ከሄዱ ግን እምነታቸውን ዘመዶቻቸው ሊያበላሹባቸው ይችላሉ፡፡

89. አንተ ቃለእግዚአብሔርን ሰምቶ ካመነ በኂላ ወደአረማዊያኑ ቤተሰቦቹ መልሰህ ከላክከው ከቀድሞ በበለጠ ክህደቱ ሊብስ ይችላል፡፡

90. በወንጌል በእግራቸው እንዳይረግጡት ተመልሰውም እንዳይነክሱአችሁ የተቀደሰውን ለውሾች አትሥጡ ዕንቁዎቻችሁንም በእርያዎች ፊት አትጣሉ ተብሎ ተፅፏል፡፡

አበዊሆሙ ክሐድያን ብሂል ዘውእቶሙ ዘማውያን ዘእንበለሕግ ወሥርዓት።

91. ወኢይሂዱ ንዋየ ቢፆሙ በዓመፃ ከመ ከለባት ወአህርውኒ ዘሰመዮሙ ለእለ አልቦሙ ሕገ አይሁድ ዘውእቶሙ አረማውያን ርኩሳን እስመ አልቦሙ ተስፋ ውስተ ምሕረት ቀዊሞሙ ውስተ ፍትሕ በከመይቤ እስመ ጊዜ ትወፅእ ነፍሶሙ እምሥጋሆሙ ይገብኡ ውስተኵነኔ

92. ወበእንተዝ ኢይትነሥኡ ኃጥአን እምደይን ወኢኃጥአን ውስተ ምክረ ጻድቃን ዝንቱኬ ኢቀደሞሙ ውስተ ቅድስና ወአልቦሙ ተስፋ ለድኂን ወለምሒር።

93. እስመሠለጡ ተስፋ ወፍግዓ በዲበ ምድር በኵሉ ምግባረ እኩይ ወገብሩ ፈቃደ ልቦሙ ወአኮ ፈቃደ እግዚአብሔር ወበእንተዝ ቦኡ ውስተኵነኔ ወኢያገብእዎሙ ውስተ ቅድስት ሐገር ወአልቦሙ ተስፋ ድሒን።

94. አ ሊቃናተ ቤተክርስቲያን ዕቀቡ ሥርዓተ ዘተወፈይክሙ እምኀበ እግዚአብሔር ወእምኀቤነ ከመ ትሑሩ በኵሉ ትእዛዝ ዘአዘዝናክሙ

95. በቀኖና ተሠርዓ ከመኢይቅስጡ ንዋየ ቤተክደርስቲያን ወኢይረስዩ ለትካዘ ርእሶሙ እምዘኮነ ከዊኖ ዘዚአሃ

ያሳመናችሁዋቸውን ሰዎች መልሳችሁ ወደቤተሰቦቻቸው አትላኩ። ከሐዲ ማለት ያለህግ በአመንዝራነት የሚኖር ሰው ማለት ነው።

91. አረማውያን የባለእንጀራቸውን ገንዘብ እንደውሾች ይናጠቃሉ አሳማዎች የተባሉትም ህግ የለሾች ሁነው የረከሱ አለማውያን ናቸው እነዚህ የድሕነት ተስፋ ፈፅሞ የሌላቸው ናቸው ጌታችንም ለፍርድ ያቀርባቸዋል። የነሱ ነፍስ ከሥጋዋ እንደተለየች ወደኩነኔ ትወሰዳለች።

92. ስለዚህም ረሲአን ከደይን አይነሱም ሐጢአተኞችም ከፃድቃን ምክር አይጨመሩም ስዚህም በተነሳ ጌታ በተቀደሰው ቦታ አያቆማቸውም የመዳንና ምሕረትን የማግኘት ዕድልም የላቸውም

93. እነዚህ ህግ የለሾች ወገኖች ተስፋቸውንና ተድላደስታቸውን ሥጋዊ ስሜታቸው በሚመራቸው ብቻ እየተመሩ በምድር ጨርሰዋል በፈቃዳቸው እንጂ በፈቃደእግዚአብሔር አይሄዱም ስለዚህ ፍዳ መከራና ሀዘን ብቻ ይጠብቁዋቸዋል እንጂ ወደቅድስና አይገቡም።

94. የቤተክርስቲያን አለቆች ሆይ ከእግዚአብሔርና ከኛ የተረከባችሁትን ሥርዓት ይዛችሁ ለመጓዝ ትችሉ ዘንድ።

95. ሰዎች የቤተክርስቲያንን ሐብት ለግላዊ ተግባራቸው እንዳያውሉ በቀኖና ቤተክርስቲያን ተወስኗል ከማንኛው የቤተክርስቲያን

ለቤተክርስቲያን እስመ፡ዘእግዚአብሔር ውስቱ ወዘቀሠጠ ዘእንበለ ፈቃደሥዩማኒ ቤተክርስቲ'ን ተዓወሮ ለእግዚአብሔር።

96. ለዘከመ፡ዝ ብእሲ ይጠፍእ ዝክሩ እምድር በሰማያትኒ ይትወደይ ኀበእንተአልባቲ ሙዓእ እስከለዓለም ወለስዩማነ ቤተክርስቲ'ን ቤተ እግዚአብሔር ኢይሕምዩዎሙ ወኢይበልዎሙ አይቴ ወሰዱ እስመበእንተ እግዚአብሔር ይሁቡ ለፅኑሳን እስመተውህቦሙ ተአምኖ እምኀበእግዚአብሔር ውስተኩሉ ንዋየቅድስት ደብተራ

97. በውስተሐላፊ ንዋየዝንቱ ዓለም እፎ ኢይትአመኖ እግዚአብሔር እንዘነአምር ከመወሀቦ መራሑተ መንግሥተ ሰማያት

98. ዕቀቡ ሥርዓታ ዘውስጥ ወዘአፍአ ለቅድስት ቤተክርስቲያ'ን ዘይትገበር በነፍስ ወሥጋ ዘሕቡእ ወዘገሀድ ከመትቁሙ ፍሱሐ ኒክሙ በዓውደከብካቡ ለክርስቶስ አመያስተርኢ በስብሐተሁ ይኩንን ሕያዋነ ወሙታነ።

99. ክርስቶስ ይሁቦሙ ለጻድቃን አስበጽድቆሙ ወለእለኢገብሩ ፈቃደ ሐጥአን ይሁቦሙ አስበ ኀጢአቶሙ ኵነኔ ነደ እሳት ወአንስ እብለክሙ አቀቡ ትእዛዘነ ዘአዘዝናክሙ ወኢትበሉ ለየማን ወኢለጸጋም።

100. እስመ እግዚአብሔር ይወቅሰክሙ በእንተ ዘኢሰነይክሙ

ኅብት በፈቃዳቸው አይውሰዱ የቤተክርስቲያን ገንዘብ የእግዚአብሔር ገንዘብ ነው ከቤተክርስቲያን ሹማምንት ፈቃድ ውጭ ገንዘብን የወሰደ እግዚአብሔርን ችላ ብሏል።

96. የቤተእግዚአብሔርን ንብረት የሚቀስጥ ሰው ከዚች ምድር ዘር አልባ ሁኖ ይነቀላል። በሰማያዊው ዓለምም እስከ ዘለዓለም ከማይወጣበት ገሐነም ይከተታል የቤተክርስቲያን ሹማምንት ገንዘቡን የት አደረሱት ተብለው መታማት የለባቸውም እነሱ የተቸገረውን እያዩ ይረዱበታልና የቅድስት ቤተክርስቲያን ኃላፊነት በሙሉም ከነሱ ራስ ላይ ነው የተጣለው

97. እግዚአብሔር የመንግሥተ ሰማያትን ቁልፍ የሠጠው ካህን በዚህ በሚያልፈው ዓለም ገንዘብ እንዴት አይታመንም

98. የቤተክርስቲያንን ሥርዓት በውስጥም ሆነ በውጭ በነፍስና በሥጋ በድብቅ የሚሠራው ሁሉ ሙታንንና ሕያዋንን ሊገዛ ክርስቶስ በተገለጠ ጊዜ በሠርጉ አደባባይ ደስተኞች ሁናችሁ እንድትቆሙ ያደርጋቹኋል።

99. ክርስቶስ ለፃድቃን የድካማቸውን ዋጋ ይሠጣቸዋል ለሐጥአን ደግሞ የሱ ፈቃድ ሳይፈፅሙ ቀርተዋልና የሐጢአተኝነት ዋጋቸውን ይከፍላቸዋል ግራና ቀኝ ሳትሉ እኛ ሐዋርያት ያዘዝናችሁን ሁሉ ፈፅሙ።

100. በተቀደሰችው ድንኳን ሊፈፀም ያለውን ሥርዓት አፈፃፀማችሁ

በቅድስት ደብተራ ወእመሰ አሰነይክሙ ወገበርክሙ ኵሎ ዘአዘዝናክሙ ትነብሩ ምስሌነ ዲበመናብርተ ሱራፌል ወትኴንኑ እለ እምታሕቴክሙ::

101. ወለእለሰ ኢገብሩ ፈቃደክሙ ፍዳሆሙ ኵነኔ ነደ እሳት እስከለዓለም አንትሙሰ ኢታስትቱ ነጊረ ወምሒረ እስከ እለተ ሞቶሙ ለእለ እምታሕቴክሙ አንትሙኒ አሰንዩ ግእዘክሙ እስከ ዕለተ ሞትክሙ ከመ ትትፌሥሑ ምስሌሁ በከብካቡ ለመርዓዊ::

102. ወትብሉ ይእተአሚረ አነ ወደቂቅየ ዘወሀበኒ እግዚአብሔር ወትትፌሥሑ ምስለ ደቂቅክሙ በመንግሥተ ሰማያት ወይእተ አሚረ የአኩትዎ ለእግዚአብሔር ወንሕነኒ ምስሌሆሙ ነአኵቶ ወለእመ ሆርክሙ በሥርዓታ ለቅድስት ቤተክርስቲያን ውእቱ ይረድአክሙ ወያፀንዓክሙ ውስተ ገቢረ ትእዛዚቲሁ ከመ ትት መሐሩ ገቢረ ፈቃዱ::

103. አፅንዑ ልበክሙ ወኢትትሀወኩ እምውጊዛት ወእመሂ እምነፋሳት ወእመሂ እምሐይለ አጋንንት፣ እመሂ በዘያስተርኢ ወእመሂ በዘኢያስተርኢ

104. እስመ ለፍርሐት መቅሰፍት ባቲ እምነበእግዚአብሔር ፈሪሃ እግዚአብሔር ባህቲቱ ዘቦቱ በቍዔት እስመ ፈሪሃ

ካልተስተካከለ እግዚአብሔር ይወቅሳቹኋል እኛ ያዘዝናችሁን ሁሉ ከፈፀማችሁ ግን ጌታችን ኢየሱስክርስቶስ በገባልን ቃል መሠረት ከሱራፌል መንበር ተቀምጠን ስንፈርድ ከበታቾቻችሁ ላይ አብራችሁን ትፈርዳላችሁ::

101. የናንተን ትምሕርት ሰምተው ለማይመለሱ የነደእሳት ኩነኔ ይጠብቃቸዋል ይህም እስከዘለዓለም ነው እናንተ ግን ከናንተ በታች ያሉትን ከማስተማርና ከመንገር አትቦዝኑ እናንተም አመራራችሁን አስተካክሉ ይህንንም እስከዕለተሞታችሁ የፀና ይሁን በሙሽራው ሠርግ ደስተኞች ትሆኑ ዘንድ

102. በዛንጊዜ እኔ እግዚአብሔር ከሰጠኝ ልጆቼ ጋር በመሆን አለሁ ትላላችሁ ከመንፈሳውያን ልጆቻችሁ ጋርም ትደሰታላችሁ በመንግሥተሰማያት በዛን ጊዜ እናንተ እነሱና እኛ በሕብረት እግዚአብሔርን እናመሰግነዋለን እናንተ የቤተክርስቲያንን ሥርዓት መሠረት አድርጋችሁ ከተመራችሁ ባለቤቱ ይረዳቹኋል::

103. ልባችሁን ንፁሕ አድርጉ ማእበል አያውካችሁ የነፋሶች ነውጥም አያውካችሁ ከአጋንንት ሐይልም ተጠበቁ ከዚሁም አልፋችሁ ከሚታየውም ሆነ ከማይታየውም ሁሉ ተጠበቁ

104. ከእግዚአብሔር እምነት ውጭ የሆነ ፍርሐት መቅሠፍትን ያስከትላል (ከእግዚአብሔር ዘንድ) ጥቅምን የሚያስገኘው

እግዚአብሔር ትዓቅብ እምኵሉ መንሱት ዘይመፅ ላዕሌሁ እመሂ በቃል ወእመሂ በምግባር ወእመሂ በዘኮነ ግብረሕሲና ዝንቱ ዓለም።

105. ጠቢበ ኵን ለገቢረ ፈቃዱ ለእግዚአብሄር እስመ ኪያከ ሐረየ እግዚአብሔር ከመ ትትለአክ ለደብተራ እንተ አጥሪያ በደሙ ከመትኩን ምስትሠራየ ኃጢአት አንተሰ ንግሮሙ ለሥዩማነ ቤክርስቲያን እመቦ ብእሲ ዘየሐድግ ብእሲቶ ወውሉዶ ዘእንበለ ይልሐቁ ወያእምሩ ፍኖተ እግዚአብሔር በምክንያተ ትዕግሥት።

106. ወእመኒ ብእሲት እንተ ትሜንን ሰብሳበ ወተሐድግ ደቂቃ ዘእንበለታልሕቅ እስመ ኢኮነ ርቱዐ ይትወከፎሙ እግዚአብሔር ለእለ ከመዝ እስመ በምክንያተ ትዕግሥት አማስኑ ደቂቆሙ ወዘሰ ይሄሉ ከመይትኀሠሥ አኮ እምድሕረአውሰበ ወወለደ አላ እምንእሱ።

107. ወእምድህረ አውሰበ ወወለደ ያልሕቆሙ ወይምሀሮሙ ወይገሥፆሙ በሠናይ ከመ ያእምሩ ፍኖተ እግዚአብሔር ወእምዝ ይትገሠፁ በንሥሐ እስከ እለተ ሞቶሙ ወእምድሕረ ነሥሑ ለእመ አበሱ ኢይበቍዖሙ ዘቀዳሚ ንሥሐሆሙ።

እግዚአብሔርን መፍራት ብቻ ነው። እግዚአብሔርን የሚፈራ ሰው ሊመጣ ካለው ጥፋት ሁሉ ይጠበቃል ጥፋት በተግባር በቃል በሌላም የዚህን ዓለም ሁኔታን በማሰብም ይመጣል።

105. አንተ የእግዚአብሔርን ፈቃድ ለመፈፀም ጥበአት ይኑርህ የሐጢአት ማሥተሥረያ ትሆን ዘንድ በደሙ ገንዘብ ላደረጋት ደብተራ ተላላኪ እንድትሆን እግዚአብሔር መርጦሀል የቤተክርስቲያን ሹማምንትንም በትዕግሥት አመካኝቶ ገና ያላደጉ ሕፃናትን የእግዚአብሔርን መንገድ ሳያውቁና ሚስቱንም የሚተው ቢኖር

106. ሴትም ትዳርዋን ትታ እመንናለሁ ብትልና በማደግ ላይ የሚገኙትን ሕፃናት ልጆቿን ትታ ብትመጣ የቤተክርስቲያን ሹማምንት እንዳይቀበሉዋቸው እስጠንቅቃቸው በዚህ መንገድ ከቤተሰባቸው የሚለዩ ሁሉ እግዚአብሔር ምንናቸውን አይቀበላቸውም ምነናን የፈለገ ሰው ሳያገባ በትንሽነቱ መመነን አለበት ትዳር መሥርቶ ከወለደ በኋላ ግን መመነን አይቻልም (ቤተሰቡን ሜዳላይ ማፍሰስ የለበትም)

107. ትዳር መሥርቶ ልጆችን ከወለደ በኋላ የእግዚአብሄርን መንገድ እያሥተማረ ያሳድጋቸው በመልካም አስተዳደግም እየቀጣና እየተቆጣጠረ ያሳድጋቸው የእግዚአብሔርን መንገድ ይከተሉ ዘንድ እስከዕለተሞታቸው ድረስም በንስሐ ይገሠፁ ንሥሐ ከገባ በኋላ እንደገና ቢበድል የቀድሞው ንሥሐው ለዳግም ጥፋቱ

108. አዝዝ እንከ ይዕቀቡ ሥጋሆሙ በንጽሕ ወኵናሙ አርአያ ለውሉደክርስቲያን ከመ ያንፅሑ ሥጋሆሙ እምኵሉ ምግባረ ኀጢአት ወእም ዝሙት ወእማውታ ወበትክ ወእምክዒወ ደም ከመ ሰብእ በጕሕሉት ወእምስታይ ደመሰብእ ዘእንበለ ፅዋዕ ወበሊዓ ሥጋቢጽ በሐሜት።

109. ወአዲ ይትዐቀቡ እምስትየወይን ዘእንበለዐቅም ወእምስካር ዘይሬስዮ ለሰብእ ዘእንበለልብ ወዘሰ እንዘኤጴስቆጶስ አው ቀሲስ አው ዲቆን ዘይኀነዲ ወይሰቲ ዘእንበለዓቅም ይከውን ፅሉመልብ

110. ካህናት ለእመኮኑ ፅሙዳነ በዝንቱ ይትመተሩ እመአርጊሆሙ ወኢይክሉ ምሂረ ወገሪረ እምድሕረአስተርአዩ በስካር ለእመዘከመዝ ካህናት ተግሕሱ እምክህነት እለይሬእዩ ካልአን ይክሉ ይትከልዑ እምዝሙት ወስካር።

111. እስመስካር ያፀልም ልበ ወያደክም ሕሊና ወይሬስዮ ለብእሲ ይኩን ማሕደረ ሊዱያብሎስ ይነፍፅ ወይርሕቅ እምኔሁ መንፈስቅዱስ። ወካዕበ አዝዞሙ ለስዩማነ ቤተክርስቲያን ከመይትገሐሱ እምቀጥዓ ወመዓት

አያገለግለውም

108. አንተ ክርስቲያኖች በንፅሕና ሥጋቸውን ይጠብቁ ዘንድ እዘዛቸው የክርስቲያን ልጆች ከሐጢአት ሥራሁሉ ማለትም ከዝሙት የሞተውንና የበከተውን ከመብላት የባለንጀራውን ደም ከመጠጣትና የወንድሙን ሥጋ ከመብላት የሰውን ደም በተንኮል ከማፍሰስ እንዲሁም ከሐሜት እንዲታቀቡ ከሌሎችም የክፉዎች ሥራ እንዲጠበቁ አድርጋቸው።

109. ከመጠን ያለፈ መጠጥን ከመጠጣት ክርስቲያኖች ይታቀቡ የሚያሠክርን መጠጥ አብዝቶ የጠጣ ሰው ልቡናውን ይረሳል በተለይ በክህነት የታቀፉት ኤጴስቆጶስ ቄስና ዲያቆን ወይንን በመጠጣት ጊዜን ማባከን የለባቸውም ወይንን ማብላዛት ልቡናን አጨልሞ ከነውረኝነት ይከታልና

110. ካህናት በሥካር ከተጠመዱ ከክህነታቸው ይወገዱ ከመዓርጋቸውም ይባረሩ ህዝብን መገሠፅና ማስተማር አይቻላቸውምና ሰክረው ከታዩ በኋላ የነሱ መወገድ ለሌሎችም ትምህርት ሊሠጥ ይችላል በዚሁ ብቻ ብዙዎች ከስካርና ከዝሙት ሊታቀቡ ይችላሉ

111. ስካር የሰውን ልቡና ያጨልማል ሕሊናንም ያደክማል ሰውን የዲያብሎስ ማደርያ ያደርገዋል ከእግዚአብሔር በረከትም ይርቃል መንፈስቅዱስ አይጠጋውም ከዚህም በተያያዘ ቤተክርስቲያን አገልጋዮች ከቁጣ የራቁ እንዲሆኑ እዘዛቸው የሰው ቁጣ

እስመመዓቱ ለብእሲ ጽድቀ እግዚአብሔር ኢያገብር

112. እመቦ እምካህናት ዘያዘልፍ ቈጠዓ ይትመተር እምክህነቱ ወለእመቦ እምሕዝባውያን ዘይከውን ስምዓ በሐሰት ንግሮ ከመይትመየጥ እምሐጢአቱ ወለእመአበየ ይትመተር እምከዊነውሉደ ቅድስት ቤተክርስቲያን

113. እመቦ ዘይድሕር ብእሲቶ ዘእንበለትዘሙ ላእሌሁ እመሂ ሕዝባዊ አዝዝዎ ይቁም አፍአ እምቤተክርስቲን ፯ ዓመተ እስመነፈቀ ዘይቤ እግዚአብሔር ብእሲ ውብእሲት ፩ሥጋ እሙንቱ ዘ፡ግዚአብሔር አስተፃመረ አይፍልት ወኢይሌሊ ወገሥፅዎሙ ኢይድኃሩ አንስቲያሆሙ፡፡

114. ለዘሰ ደሐረ ብእሲቶ በግፍዕ ወኢተመይጠ በቀኖና ቤተክርስቲያን ምትርዎ እምቤተክርስቲያን

115. ወእመቦ ዘኢያከብር አባሁ ወእሞ ወኢያከብር በፍርሐተ እግዚአብሔር ይትገሠፅ በሊቃውንተ ቤተክርስቲያን

116.. ለዘከመዝ ብእሲ እምቅድመይሰደድ እምቤተክደርስቲን ያቅምዎ አፍአ እምቤተክርስቲያን ፲ ወ፪ ዓመተ፡፡

117. ወለእመቦ ዘቀተለት ምታ በሥራይ ወለእመተአምረት በዝ

የእግዚአብሔርን ክብር መግለጫ ሳይሆን ሰዎችን ተስፋ በማስቆረጥ ከቤተክርስቲያን የሚያርቅ ነው፡፡

112. ከካህናት መካከል መቆጣትን የሚያዘወትር ካለ ከክህነቱ ይመተር ከህዝባውያን ውስጥ በባለንጀራው ላይ በሐሰት የሚመሠክር ካለ ከሐጢአቱ እንዲመለስ ምከረው ለመመለስ ፈቃደኛ ካልሆነ ግን ለሌሎች ክርስቲያኖች መጥፎ አርአያ ከመሆኑ አስቀድመህ ከቤተክርስቲያን ልጅነት ይሠረዝ

113. ሳታመነዝርና በዝሙት ሳትያዝ በትዕቢት ሚስቱን የሚፈታ ሁሉ ሕዝባዊም ሆነ ሌላ ከቤተክርስቲያን ለሰባት ዓመት ይከልከል እግዚአብሔር አንድ ያደረጋቸውንና አንድ ሥጋ መሆናቸውን የተናገረላቸውን እሱ እንዲለያዩ አድርጓልና፡፡ ሌሎችም ሕዝባውያን ሚስቶቻቸውን በግፍ እንዳይፈቱ አስተምሩአቸው፡፡

114. ሚስቱን ፈትቶ ሲያበቃ በትምህርትና በቀኖና አልመለስም ካለ ከቤተክርስቲያን አባልነትና ልጅነት ተመትሮ ይባረር፡፡

115. አባቱንና እናቱን የማያከብር ካለ በቤተክርስቲያን ካህናት ይመከር ይገሠፅም አልመለስም ካለ ከቤተክርስቲያን ይባረር

116. ነገርግን በዚህ በደል የተገኘ ሰው ከቤተክርስቲያን ከመባረሩ አስቀድሞ ለአሥራሁለት ዓመት ከምእመናን ተለይቶ በውጭ ይቆይ

117. ቤት ሁና ባልዋን በሥራይ ወይም በመርዝ የገደለች ብትኖርና

ግብር ትትከላእ እመቤተክርስቲያን እስከእለተሞታ ወኢየሀብዋ ሥጋሁ ወደሞ ለክርስቶስ።

118. ወለእመነሥሐት ትፁም ኩሎመ ቁዕለሕይወታ እስከእለተሞታ ዘእንበለመባልዕት ዘቅብዕ በጊዜ፱ ሰዓት ወአልቦ ተደምሮ ምስለሕዝብ ወበእንተፍቅረሰብእ ይድግሙ ላቲ ጸሎተንሥሐ በእለተሞታ ከመይሥረይ ላቲ እግዚአብሔር ሐጢአታ ወትድሐን በዕለተደይን።

119. ወካዕበ አዝዝዎሙ ህገ ዘቤተክርስቲያን ለነገሥደት ወለመኳንንት ወለዕቡያን ወለዝሑራን እለመፅኡ በትምይንት ላእለካህናተ ቤተክርስቲያን ይህድጉ እኩየ ምግባሮሙ ወኢይሑሩ በዝ ወያዕምሩ ከመቦ አምላክ ዘይመልክ ነገሥተ ወያደክም ሥልጣነ ዕቡያን በከመኦዝያን በትዕቢቱ አምፅአ ለምፅ።

120. ወሶበርእዮ ኢሳይያስ ነቢይ ለኦዝያን ንጉሥ ኢገሠፆ ተሠወሮ ራእየእግዚአብሔር ለኢሳያስ ነቢይ ወሶበሞተ አዝያን ንጉሥ አስተርአዮ እግዚአብሔር ከመቀደሚ ለኢሳይያስ ነቢይ።

121. ወበእንተዝ ይቤ በዓመተሞተ አዝን ርኢክዎ ለእግዚአብሔር ህያው እንዘይነብር ዲበመንበሩ ልዑል ወነዊኅ ወምሉእ ቤተ ስብሐቲሁ ሱራፌል ወኪሩቤል ይኬልልዎ ወመንክር ስሚያተስብሐቲዮሙ።

ይህንንም አድራጎቷ ከታወቀ እስከመጨረሻው ከሥጋወደሙ ትከልከል እስክትሞትም እንደተባረረች ትቅር

118. በንሥሐ መመለሷን ካረጋገጠች ግን ከቅቤ ከወተትና ከመሳሰሉት ጥሉላት መባልዕት ተከልክላ ደረቅም ግብን በዘጠኝ ሰዓት እተመገበች እስከዕለተሞቷ ትኑር እግዚአብሔር ይቅር ይላት ዘንድም በዕለተሞቷ ፀሎተንሥሐ ይደገምላት (ለተመልካችም ተብሎ)

119. ነገሥታትንና መኳንንትን በቤተክርስቲያን ህግ እንደሌላው ተራ ህዝብ መሆናቸውን እስኪረዱ ድረስ ትምህርትን ሥጡአቸው በትዕቢትና በትዝሕርት ወደቤተክርስቲያን እንዳይመጡም አስተምሩአቸው ከምድራዊ ሥልጣን ጋር የተያያዘ እንዳይታበዩም አድርጉ ኦዝያን በትዕቢቱ ለምፃም ሆነ

120. ኢሳይያስ ነቢይ ኦዝያን ንጉሥ በመሆኑ ስላልገሠፀው በሱ ላይ አድሮ የነበረውን ሐብተትንቢት ተሠወረበት ኦዝያን ከሞተ በኋላ ግን ለኢሳይያስ ሐብተትንቢቱ ተመለሰለት።

121. ስለዚህም "ኦዝያን በሞተበት ዓመት ሕያው እግዚአብሔርን በልዑል መንበሩ ላይ ሆኖ አየሁት መንበሩ ረጂም ነው ምሥጋናውም ምሉዕ ነው ሱራፌልና ኪሩቤልም ያመሰግኑታል ምስጋናውንም መስማት እጅግ አስገራሚና የሚደነቅ ነው።"

22. ርእዩኬ ከመተምያ እግዚአብሔር ለኢሳይያስ ኒቢይ በእንተዘኢገሠያ ለአዝያን ወከመሁ አንትሙኒ ሥዩማነቤተክርስቲን ገሠፅዎሙ ለነገሥት ወለመኳንንት ሶበመፅኡ በትዕቢት ውስተመካነምሥዋእ።

123. ወአዲ በእንተእከየምግባሮሙ አርትዕዎሙ ወኢትፍርህዎሙ ውስተ እዘዘ እግዚአብሔር እስመብክሙ አምላክ ዘይገርም እምኔሆሙ ወእመሰ አኮ ፪ክሙ ትትኬኑ።

12፬.፣ አንትሙኒ ነገሥት ወመኳንንት እፎ ኢትሰምዑ ቃለካህናት ዘነገሩክሙ እስመአፈእግዚአብሔር ብሂል ካህናት እሙንቱ ኢታስተሐቅርዎሙ እስመሰብዓዐይን እሙንቱ በሀገር ዐባይ እንተበሰማያት።

125. ተዘከሩ ከመአጥመቆ ዮሐንስ ለኢየሱስ እንዘገብሩ ውእቱ ወበእንተዝ አክብሩዎሙ ለመምህራነቤተክርስቲያን አ ካህናት ኢትፍርሑ ገሠፃቶሙ ለሐጥአን በኩሉ ዘርኢክሙ ወሰማዕክሙ ኃጢአቶሙ።

126. እመበ እምሥዩማነቤተክርስቲያን ዘይነሥእ ብፅአተ ወበኩራተ ወኢይሁብ ለነዳያን ወለግዩራነቤተክርስቲያን አላ

አለ።

122. ኢሳይያስ አዝያንን ሳይገሥፀው በመቅረቱ እግዚአብሄር እንዴት እንደተቆጣው ተመልከቱ ይህንን በመገንዘብ እናንተም ነገሥታትንና መኳንንትን ሳትፈሩ ገሥፁዋቸው ወደመካነምሥዋዕ በትዕቢት ሲመጡ ዝም አትበሉዋቸው

123. ዳግመኛም ስለመጥፎተግባራቸው እየተከታተላችሁ ቀናመንገድን እንዲይዙ አድርጉ አትፍሩዋቸውም የእግዚአብሔርን ትእዛዝ በተመለከተ እነሱን ከመገሠፅ ወደኋላ አትበሉም ከነሱ በበለጠ ታላቅ ግርማ ያለው አምላክ መኖሩን አትርሱ

124. እናንተም ነገሥታት ና መኳንንት ለምን ቃለእግዚአብሔርን አትሰሙም ለምን የካህናትን ምክር አትቀበሉም ካህን ማለት የእግዚአብሔር አፍ ማለት ነው ካህናትን አታቃልሉዋቸው በመንግሥተሰማያት ያለች አገር በርከፋቾች እነሱ ናቸው

125. ዮሐንስ ለኢየሱስክርስቶስ ከፍጡሮቹ አንዱ ነው ነገር ግን ፈጣሪውን ለማጥምቅ ቻለ ስለዚህ መኳንንት የሆናችሁ ሁሉ የቤተክርስቲንን መምህራን አትናቁዋቸው ተገቢውን ክብር ስጡአቸው እንጂ እናንተም ካህናት ሰዎች ሓጢአትን እየሠሩ እያያችሁ ዝም አትበሉ ገሥፁዋቸው እንጂ

126. ከቤተክርስቲያን ሐላፊዎች ሹማምንት ሥእለትንና ብፅአትን ተቀብሎ ከተቀበለው የብፅአትና የሥእለት ገንዘብ

ይገብር ለትካዘቤቱ ይትመተር እመአርጊሃ ለቅድስት ቤተክርስቲያን ወኩሉ ዘያቀልል ግዘተ እምጳጳሳት፣ ቀሳውስት ወዲያቆናት አልቦቱ ፍትሕ እምኀበዘአውገዞ ወዘተውክፎ እምባእዳን መኳንንት ለሊሁ ይትኳነን ምስሌሁ

127. ወእመሂ በግፍዕ ተኮነነ ይስኪንበ መንበሩ ለሊቀጳጳሳት ወካዕበ ይትጋብኡ ሎቱ በእንቲአሁ ወይቤይኑ እመሂ በግፍዕ ተኮነነ ያግብዕዎ ኀበዘቀዳሚ መአርጊሁ።

128. ወኢይሁር ቀሲስ ውስተሰብሳብ ዳግም ዘ፪ተ አውሰበ ከሚኢይቅስፎ እግዚአብሔር በመዓቱ ወኢይትሐወል ውስተምሳሐቲሆሙ ለሐጥኣን ወአዲ ኢይባርክ ቤቶሙ ወበዓሎሙ ወውሉዶሙኒ ኢይሠመር ለግብረ ክሕነት እስመደቂቀሀድገት እሙንቱ

129. ወእመኒ አብኡ ስንዳሌ ወዕጣነ ከንቱ ወርኩስ ውስቱ በኀበእግዚአብሔር ፀሎቶሙኒ ኢውክፍት ቅድመእግዚአብሔር አንትሙ ካሕናት አዝዝዎሙ ከመይትገሐሱ እምርኩስ ወዝሙት፣ ከመይትባረክ ዘርአሙ ወውሉዶሙ በቃለዚአክሙ።

130. አንትሙኒ ከመትኩኑ ሱቱፋነ ውስተዓለም ሠናይ

።በቤተክርስቲያን ለወደቁ ነዳያን የማያካፍል በአንፃሩ ለቤቱ ጥቅም የሚያውለው ከቅድስት ቤተክርስቲያን ሥልጣኑ ይባረር ማንኛውም ከቤተክርስቲያን የተላለፈውን ውግዘት የሚያቃልል ወይም ተወግዞ የተለየውን ሰው የሚቀበል ከሱ ጋር ውግዘቱን ይቀበላል።

127. የተኮነነው ወይም ከሥልጣኑ ሲወገድ የቻለው በግፍ መሆኑን ከገለፀ በይግባኝ የጳጳሳት ጉባኤ ካሉበት ይሂድ ጳጳሳቱም የቤተክርስቲያንን ቀኖና በሚያዘው መሠረት ፍትሐዊና መንፈሳዊ ዳኝነትን በማስተላለፍ ይወስኑለት በግፍ ከሥልጣኑ ከተባረረ ይመልሱት።

128. ቄስ ዳግም ሁለተኛ ጋብቻን ወደሚፈፅሙ ሰዎች ቤት አይሂድ ይህን ካደረገ የእግዚአብሔር መቅሰፍት ያገኘዋል ቄስ የሐጢአተኞችን ግብዣ አይቀበል ከነሱ ጋርም አይቀላቀል። በዓላቸውንም አይባርክ የነሱንም ልጆች ለክህነት አይምረጥ ልጆች እንደወላጆች ናቸውና።

129. ሥንዴንና ዕጣንን ይዘው ወደቤተእግዚአብሔር ቢያመጡ የነሱ መባ የረከሰ ነውና አትቀበሉዋቸው እግዚአብሔር ይህን የመሰለ መባ አይቀበልምና ሰዎች መባ ከማምጣታቸው አስቀድመው ራሳቸውን ንፁሕ ያድርጉ ዘንድ አስተምሩአቸው ከዝሙት ከሌላ ርኩሳት ይራቁ ልጆቻቸው ይባረኩ ዘንድ

130. እናንተ ካህናት ግን የመልካሙ መንግሥተ ሰማያት ሕይወት

እለመሐርና ክሙ ወገሠፅናክሙ ወአግባዕናክሙ ውስተዘበዓማን ፍኖተመድሐኒት

## ምዕራፍ ፲ ተግግሣፅ ወምክር ለውሉደክርስቲን እምኀበጴጥሮስ

1. ንግርዎሙ ለስዩማነቤተክርስቲያን ከመይንግሩ እመቦ ዘተረክበ በዝሙት ወእመሂ በሐዊረብእሲተብእሲ ወእመሂ በአዘምዎድንግል ወእመሂ ዘወለደ እምኀበዘማት ለእመአምነ ጌጋዩ ወተዘልፈ በስምዕ ወለስምዕኒ እመእሙን ቃሉ እምእለ አልቦሙ ሐሰት።
2. ይትመተር እመአርጊሃ ለቅድስት ቤተክርስቲያን።
3. ወአዲ ዘበሰማያትኒ ከላእነ ከመኢይባኡ እስመመራትተ መንግሥተሰማያት ሀሎ በሀቤነ ውስተእዴነ ወበቃልነ ይትመተሩ ኲሎሙ ገብርተ ዓመፃ እለኢአቀቡ ሥርዓታ ለቅድስት ቤተክርስቲያን ይኩኑ ፍሉጣነ እምኖኀተዐንቀፀብርሃን።
4. (ሀ) እስመአነ ጴጥሮስ መንፈሳዊ አቡክሙ ዘሰመየኒ እግዚአብሔር እግዚእነ ኮኲሐ ከመ ትትሐነጽ ዲበ መሠርትየ በሃይማኖት እንዘ ውእቱ መሠረትየ ሊተኒ በክሂሎትየ ዘንተ ሠራዕኩ ከመ ኢይትአደውዋ ለቅድስት

ተሳታፊዎች ትሆኑ ዘንድ ያስተማርናችሁ ናችሁ ገሥፀንም የመድሐኒት መንገድ ወደሆነችው ቦታ አስገብተናቹኋል።

## ምዕራፍ ፲ ከጴጥሮስ ለውሉደ ክርስቲያን የተሠጠ ተግሣፅና ምክር

1. በዝሙት የተገኘ ቢኖር ትዳር ያላትን ሴት ያማገጠ ወይም ደግሞ በድንግልና የሚገኙትን ሴቶች ለጥቅም ብሎ አሳልፎ ለዝሙት የሚሠጥ ከዚሁ ጋር በተያያዘ መንገድ ከአመንዝራ ጋር በመገኛኘት ልጅን የወለደ ሲገኝ ድርጊቱን ካመነ አመነ ካላመነ ደግሞ ሃይማኖት ያላቸውን ሰዎች በሚሠጡት ምሥክርነት።
2. በቤተክርስቲን ያለው አባልነት እንዲቋረጥ ያደርጉ ዘንድ ለካህናት ንገራቸው።
3. በሰማያትም መግቢያ እንዳይኖራቸው የመንግሥተሰማያት ቁልፍ ለኛ ሠጥቶአል ስለዚህ በኛ ሥልጣን ይከለከላሉ በቃላችንም ዐመፀኞች ሁሉ ይወገዛሉ የቤተክርስቲያንን ሥርዓት አልጠበቁምና በብርሃን በር ርቀው የተጣሉ ይሁኑ
4. (ሀ) እኔ ጴጥሮስ መንፈሳዊ አባታችሁ ነኝ በዚህም የሾመኝ ጌታችን መድሐኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ነው አለት ተብየ በሱ ዘንድ ተሾሜ አለሁ እናንተ በኔ መሠረትነት ትታነፁ ዘንድ እኔም በተሠጠኝ ችሎታ ይህንን ሠራሁ ቤተክርስቲያንን

ቤተ ክርስቲያን እንተ እግዚእየ ወአምላኪየ ኢየሱስ ክርስቶስ

4. (ለ) አፅንዕ ሥርዓተ ዘሠራዕኩ ለከ ኦ ወልድየ ቀሌሚንጦስ ወኢታለብዎሙ ለእለ አልቦሙ አእምሮ ከመኢይኩን ነገረ እግዚአብሔር ስላቀ በኀቤሆሙ እንዘ ያስተካብዱ ወያስተአብዱ ትእዛዘ ዘአዘዝክዎሙ በእንተ ቤተክደርስቲያን ወበእንተ አምላኪየ።

5. ወለሲሞን መሠርይ አፅደፍክዎ በውእቱ መዋዕል በእንተ እኩይ ምግባሩ ወለሐናንያ ዘቀሠጠ ሴጠ ወይን አነ ረገምክዎ ወሶቤሃ ነሥአ መልአክ መጥባህተ ቀትል ዘበጦ ወሞተ በአሐቲ ዝብጠት ወከሮገሁ ብእሲቱኒ ሞተት እምድሕሬሁ።

6. እስመ ተዐደው ሥርዓታ ለቅድስት ቤተ ክርስቲያን ለዘየሐውር በንፁሕ ኤጵስቆጶስ ሕልው ምስሌሁ መልአከ እግዚአብሔር ወይገብር ሎቱ ፈቃዶ።

7. ወበእንተዝ አሠንዩ ደቂቃ ለቤተክርስቲያን በኩሉ ግብርክሙ ዘትገብሩ ለእለ አልቦሙ አእምሮ ወኢያስተሐቅሩ ትእዛዘ እግዚአብሔር

8. ወግበር ሥርዓታ ለቤተክርስቲያን ከመ አርአያ ኢየሩሳሌም ሰማያዊት እንተ በውስቴታ ይሴብሑ መላእክተ እግዚአብሔር ዘእንበለ ፅርዓት ወኢይፈቅድ እግዚአብሔር

እንዳትደፋፈሩዋት እሷ የጌታየና አምላኬ ኢየሱስ ክርስቶስ ናትና።

4. (ለ) ልጄ ቀሌሚንጦስ ሆይ የሠራሁልህን ስርዓት በጥንቃቄ ጠብቅ አእምሮ ለሌላቸው የጠለቀውን ምሥጢር አትግለፅላቸው የእግዚአብሔርን ቃል መዘባበቻ እንዳያደርጉት ያልሆነውን ትርጉም እየሠጡ የተሠጣቸውን ስለአምላክና ስለቤተክርስቲያን ትእዛዝ በክብር መከተል ፈቃድ የላቸውም።

5. መሠርዩ ሲሞንን በእግዚአብሔር ኃይል እንዲወድቅ አደረግሁት የወይኑን ሺያጭ ያታለለ ሐናንያንም እኔ ረገምሁትና ወድያው መልአክ የኔን ርግማን ተቀብሎ መታው እሱም ባንድ ጊዜ ሞተ ሚስቱም ከሱ በኋላ ሞተች።

6. እነሲሞን የቅድስት ቤተክርስቲያንን ሥርዓት ስለ ተደፋፈሩ ሞቱ በንፁሕ ለሚመራ ኤጵስቆጶስ የእግዚአብሔር መልአክ አይለየውም ፈቃዱን ይፈፅምለታል።

7. ስለዚህ የቤተክርስቲያንን ልጆች በትክክል ምሩ በሥራቸው ሁሉ ለእግዚአብሔር እንዲገዙ ልቡና የሌላቸው ሰዎች ግን እግዚአብሔርን ቃል ያቃልላሉ።

8. የቤተክርስቲያንን ሥርዓት በሰማያዊቷ ኢየሩሳሌም ምሳሌ አድርግ ሰማያዊቷ ኢየሩሳሌም መላእክተእግዚአብሔር ያለዕረፍት ምሥጋና የሚያቀርቡባት ናት እግዚአብሔር የተንኮለኞችን ነገር

ነገረ ጽልሕዋን ወአማፅያን።

9. እስመ ቅዱስ ውእቱ ወይትቄደስ በቅዱሳን ወኢይፈቅድ ከናፍረ ጉሕሉት እስመ በቅዱሳን ይሴባሕ ወበንፁሐን ይትዌደስ ወበትጉኃን ይትሌአል ወመሥዋ እተኃጥአን ኢይሠምር።

10. እመቦ ኤጲስቆጶስ ውስተ ጵጵስና ወጳጳስ፣ ውስተ ሊቀጳጳሳትና ወዲያቆን ውስተ ግብረ ክህነት ወንፍቀ ዲያቆን ውስተ ዲቁና ወአናጉንስጢስ ውስተ ግብረ ንፍቀዲያቆናት ወሕዝባዊ ውስተ ግብረ አናጉኒንስጢስ ወዲያቆናዊት ውስተ ግብረ ሕዝባዊ፣ ወደናግል ውስተ ግብረአንስት ወአዋልድ ውስተ ግብረደናግል።

11. ወኵሉ ዘይትአደው እምዘ ዘከርነ መዓርጊሃ ለቅድስት ቤተክርስቲያን ውጉዝ ውስቴ ወይትመተር እመአርጊሃ ለቅድስት ቤተክርስቲያን

12. ለእመእባእናሁ ንሕነ አልብነ ሥልጣን ወልአከ እግዚአብሔር ይትመዓፅ ላእሌሁ ወየሐንቅ ከመ ይሁዳ ዕልው ዘተፈልጠ እማሕበርነ ወተሐንቀ በከመ መሀሮ ሰይጣን አቡሁ።

13. እመቦ ዘተሐየለ ካልኡ ወዘአፅቀቦ ንዋዩ በዓመፃ እመሂ እም እንስሳ ወእመሂ እምንዋየ ባእድ አው ወርቀ ወብሩረ ይፍዲ

አይቀበልም

9. እግዚአብሔር ቅዱስ ነውና በቅዱሳኖቹ ይመሠገናል የተንኮለኞችን ምሥጋና አይቀበልም እሱ በቅዱሳኖቹ ብቻ ይመሰገናል በንፁሐኖቹም ይወደሳል በትጉሐንም ከፍከፍ ይላል የሐጥአንን መሥዋዕት አይቀበልም

10. ኤጵስቆጶስ ሁኖ የጳጳስን መዓርግ ጳጳስሁኖ የሊቀጳጳስን መዓርግ፣ ዲያቆን ሆኖ የቄስን መዓርግ ንፍቀዲያቆን ሆኖ የዲያቆንን መዓርግ፣ አናጉንስጢስ ሆኖ የንፍቀዲያቆንን መዓርግ፣ ሕዝባዊ ሆኖ የአናጉስጢስን መዓርግ፣ ዲያቆናዊት ሁና የሕዝባውያንን መዓርግ፣ ሴቶች ሆነው የዲያቆናዊትን መዓርግ፣ ደናግል ሁነው የሴቶችን መዓርግ፣ ልጃገረዶች ሁኖው የሴቶችን መዓርግ

11. ከነዚህ ከዚህ በላይ የተዘረዘሩትን ሁሉ በድፍረት የፈፀመ የተወገዘ ይሁን ከቅድስት ቤተክርስቲያን የተረከበውንም መዓርግ ተቀምቶ ይቅር በማንኛው ቤተክርስቲያን አይገኝ።

12. እኛ በነዚህ ዐመፀኞች ላይ ሥልጣን የለንም የእግዚአብሔር መልአክ ግን በሱ ላይ ቁጣውን ያሳያል እንደይሁዳም ያሳንቀዋል ይሁዳ በገዛራሱ ታነቀ ይህም ካባቱ ሠይጣን የተማረው ነው።

13. ከሰው በአደራነት ገንዘብንም ሆነ እንስሳ፣ ወርቅም ይሁን ብር አልመልስም ብሎ ያመፀ ቢኖር በአደራነት ከተረከበው ዕጥፍ

ካዕበተ።

4. ወለእመ ተሐበለ እምንዋየ ቤተክርስቲያን የሀብ ትሕምስተ እስመ ተሐየለ ንዋየ ቤተ ክደርስቲያን ወዐመፀ ቤተእግዚአብሔር ዘንተ ሠራዕነ በቀኖና ከመ ኢይትኀየል ፩ ንዋየ ካልኡ

5. እመቦ እም ኤጴስቆጳሳት ቀሳውስት፣ ወዲያቆናት ዘይነሥኡ ርዴ ወበርዴኒ ያመክዕብ ንዋዮ ይትምተር እመዓርጊሃ ለቤተክርስቲያን ወይሠዐር እምዘኮነ ሢመቱ ወእመቦ እምኤጴስቆጳሳት ቀሳውስት ወዲያቆናት ዘያስተዋዲ ቢያ በዓመፃ ኀበ ነገሥት ወመኳንንት ወይሰኪ በእንተ አበሳ ዘአበሰ ሎቱ ይትመተር እመዓርጊሁ።

16. እመቦ እምእመናን ዘይድሕር ብእሲቶ ዘእንበለ ትዘሙ በላእሌሁ ወያወስብ ሕድግተ ይቁም እስከ ይኔስሕ እመቦ እምክርስቲያን ዘየሐውር ኀበ ዘፈን ወተውኔት ወይበውእ ውስተ ቤተ ተውኔት ወይሰክር ወይበውእ ቤተ ብለኔ ይትመተር እም ቤተክርስቲያን።

17. እመቦ እምውሉደክርስቲያን ዘቦአ ምኩራበአይሁድ ወምኩራበ አሬሚ ይጸሊ ምስሌሆሙ ወይበልዕ እምበዓሎሙ ወመሥዋዕቶሙ ይትመተር እመዓርጊሃ ለቤተክርስቲያን።

18. እመቦ ኤጴስቆጶስ፣ ቀሲስ አው ዲያቆን ወሕዝባዊ እለየአምኑ በነገረ ረዓይያን ኮከብ ወመጥዓውያን ወመሠግላን

አድርጎ ይክፈል።

14. በዚሁ አካሄድ የቤተክርስቲያንን ገንዘብ በዓመፅ ወስዶ ለግሉ መጠቀምያ ያዋለው አምስት ዕጥፍ አድርጎ ይክፈል። የበደለውም ግለሰብ ሳይሆን ቤተእግዚአብሔር ስለሆነ ይህን ቀኖና ሠርተናል አንዱ የሌላውን ገንዘብ እንዳይቀማም ቀኖና ሠርተናል

15. ኤጲስቆጶስ ሁኖ ወይምቄስ ዲያቆንም ይሁን በአራጣ ገንዘቡን እየሠጠ ዕጥፍ በማድረግ የሚቀበል ከሥልጣኑ ይመተር ከቤተክርስቲያን ሥልጣኑም ይወገድ ከኤጴስቆጳሳት ቀሳውስትና ዲያቆናት መካከል ባለንጀራውን በበደል ተነሳስቶ ወደነገሥትና ወደመኳንንት ቢከስ ካለበት የቤተክርስቲያን ሹመት ይውረድ ከአገልግሎቱም ይወገድ።

16. ሚስቱ አመንዝራ ሳትሆንበት የሚፈታና የተፈታችውም ያገባ ንሥሐውንእስኪጨርስ ድረስ ወደቤተክርስቲያን ከመግባት ይከልከል ክርስቲያን ሆኖ እያለ ዘፈን ወዳለበትና ሥካር፣ ዝሙት፣ መዳራት ወዳለበት ቤት ከሄደ ከክርስቲያንነትም ሆነ ከማናኛውም አባልነት ይሠረዝ

17. ከክርስቲያን ወገኖች ወደ አይሁድና ወደአረማውያን ምኩራብ ገብቶ በነሱ የአምልኮት ሥርዓት የተሳተፈ ለበዓላቸው ከተሠዋውም መስዋዕት የበላ ከቤተክርስቲያን ይወገዝ።

18. ኤጲስቆጳሳት ከቀሳውስት፣ ከዲያቆናትና ከሕዝባውያን በኮከብቆጣሪዎች በጣኦት ማምለክ ከወደቁ ከቤተክርስቲያን

ወይትፋቀሩ ምስሌሆሙ ይትመተሩ እምቤተክርስቲያን ወለእመ አስገሉ በእሳት ወማይ ወበአእዋም በዝኒ ይትመተሩ እም ቤተክርስቲያን።

19. ወእመሰ ሕዝባዊ ይቁም እምቤተክርስቲያን እስከይኔስሕ ወይትወሐድ ውስቴታ በጸሎት ወበስእለት በአንብዕ።

20. ቤተክርስቲያን አምሳለሐመር ዘይዘብጥዋ መዋግደ ወነፋሳት ወማዕበላት ወኢትትሐወክ በእንተ ዘተገብረት በእደኪያን ወትትሔደፍ ኢትትህወክ ወኢታንቀለቅል ወኢትሠጥም እምአበሳሆሙ ለመምዕልያን ነገሥት።

21. ዲበ ሃይማኖተ መስቀል ተሐንጸ መሠረታ ወኖትያትኒ በየማና ወበፀጋማ እለየሐድፉ ኪየሃ እስከ ትበፅህ ኀበ መርሶ መድኅኒት ወምሳሌሃ ለባሕር ዓለም ውስቱ ወመዋግድ ወማዕበል ወነፋሳት እሙንቱ መጥዐውያን ወመሰግላን እለ የሀውኩ ዓለመ በምልኡ።

22. እሙንቱሂ ምስለ ዘይሰምዖሙ ይወርዱ ውስተ ባሕረ እሳት ወይትሐተሙ ውስቴታ ኀበ አልባቲ ሙዳእ እስከ ለዓለም።

23. ወካዕበ ንሕነ እሙንቱ እለ ንፀይሕ ፍኖታ ለሐመርነ ቅድስት ቤተክርስቲያን ወንፀሐይሕ አስዋከ ረሲአን እምኔሃ

ይባረሩ ይወገዙ ከተጠቀሱት ጋር ፍቅር ካላቸውም ይባረሩ በእሳት በውሃ በዛፍና በሌሎችም ከማምለክ ደረጃ ላይ ከደረሱ ከቅድስት ቤተክርስቲያን አባልነታቸው ተወግዘው ይለዩ

19. ሕዝባዊው ብዙ ትምህርትን ካለማግኘቱ የተነሳ ይህንን ፈፅሞ ከሆነ ንሥሐ እስኪገባ ድረስ በሰቆቃና በልቅሶ በቤተክርስቲያን ዙርያ ይመለስ።

20. ቤተክርስቲያን በመልካም ጥበበኛ ተሠርታ በመልካም ጥበበኛ እንደምትነዳና መዋግድ፣ ማእበላትና ነፋሳት ከክፉዎች ነገሥታት ጥፋት የተነሳ በማትሠጥም መርከብ ትመሰላለች ቤተክርስቲያን በምንም በምን የማትናወጥ የፀናች ናት።

21. ቅድስት ቤተክርስቲያን በሃይማኖት መስቀል ላይ የተመሠረተች ናት መሠረቷም ፅኑዕ ነው። በግራዋና በቀኟዋ ዋናተኞች ያጅብዋታል ከምትንሳፈፍበት ባህር አልፋ ወደመርሶ መድሐኒት እስክትደርስ ድረስም ከሷ አይርቁም የባሕር ምሳሌ አለም ነው በነፋስ በመዋግድና በማዕበል የተመሰሉት ደግሞ ጠንቋዮችና ሌሎችም ናቸው እነሱ ዓለምን የሚያውኩ ናቸው።

22. እነዚህ ዐመፀኞች እነሱን እየተከተሉ ምክራቸውን ከሚሰሙና በነሱም ምክር የጥፋት ጎዳናን ከሚመርጡ ጋር ወደዘለዓለምጥፋት ይገባሉ።

23. የኛ መርከብ የሆነችውን የቤተክርስቲያን መንገድ የምንጠርግ እኛ ነን የልበዝንጉችንንም እሾህ ከቤተክርስቲያንና

ወእም አልባቢሆሙ ለእለ ያጥዕው ከመያማስኑ ቢጾሙ እሙንቱኒ ምሱናን እሙንቱ ወይትማልኡ ምስሌሆሙ ካልአነ ውስተ ኩነኔ ለእመ ረከቡ ዘኢነቅሐ ለግብረ መልእክትነ ውስተ ቅድስት ቤተክርስቲያን።

24. እስመ እምኵሉ ኀጢአት የአኪ ሠገል ወጣዖት በኀበ እግዚአብሔር ይእዜኒ መምህራነ ቤተክርስያን ውስተ ዘዚአነ ቀኖና ኢታስትቱ ገሥጽዎሙ ለእለስሕቱ ሕዝበ ክርስቲያን ከመ ኢይትመዐዕክሙ እግዚአብሔር አመትበፅሑ ቅድሜሁ።

25. ፈድፋደ ተጠናቀቁ ባቲ ከመኢትሕልፍ ሰዓት እንተባቲ ይወኅስክሙ እግዚአብሔር በእንተ ዘኢያሰነይክሙ መልእክተክሙ እስመገብር ዘየአምር ፈቃደ እግዚኡ ወኢይገብር ብዙሕ መቅሰፍቱ ወዘሰ ኢየአምር ሕዳጥ መቅሰፍቱ።

26. አርትዑ ፍናዊክሙ ኦ ውሉደ ቤተክርስቲያን ወዕቀቡ ዘሠራዕነ ለክሙ በቃለ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ።

27. አንትሙ ጳጳሳት ኢትሢሙ ዘረከብክሙ ዘእንበለ ሕግ ወዘእንበለትሕትቱ ወትጤይቁ እለቦሙ ነውር ዘነገርጋር ለእመ ኢሰምዐ ወኢተናገረ ምንተ አሰነየ ግብሮ ዘለምፅ ኢይሰየም ውስተ ቤተክርስቲያን ከመ ኢያስቆርሩ ሕዝብ

ባለእንጀራቸውን ወደጥፋት ከሚያስገቡ ጥፋተኞች የምንነቅል እኛ ነን ለጥፋት ሆን ብለው የተሠለፉ ሰዎች ብቻቸው አይጠፉም እግረመንገዳቸው ያልነቃውንና ከኛ ትእዛዝ ወደኋላ ያለውን ይዘው ይጠፋሉ እንጂ

24. ከሐጢአት ሁሉ ጣዖትን ማምለክና ጥንቆላ በእግዚአብሔር ዘንድ ይጠላል ስለዚህ የቤተክርስቲያን መምህራን ሆይ የኛን ቀኖና ተመርኩዛችሁ አስተምሩ ሥሕተት ውስጥ የገቡትንም ሕዝበክርስቲያን ከመገሠፅ አትቦዝኑ ይህን ካልፈፀማችሁ እግዚአብሔር ከፊቱ አቁሞ ይቆጣቿኋል።

25. እንድትሠሩባት እግዚአብሔር የወሰነላችሁን ሰዓት ሳታልፍ ኃላፊነታችሁን ተወጡ ዘተሠጣችሁ ሰዓት ባትሠሩ ለወቀሳና ለከባድ ቅጣት ትዳረጋላችሁ እያወቀ ሳጠፋና የጌታውን ትእዛዝ ሳልፈፀመ አገልጋይ ከባድ ቅጣት ሲጠብቀው ሳላወቀ ደግሞ ቅጣቱ ጥቂት ነው።

26. የቤተክርስቲያን ልጆች ሆይ መንገዳችሁን አስተካክሉ የጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ቃል መሠረት አድርገን የሠራንላችሁንም ጠብቁ

27. እናንተ ጳጳሳት በሕዝብ ዘንድ ታአማኒነት የሌለውን ሰው በክህነት አትሹሙት ስለሚመረጠው (ለክህነት) ከሌሎች ብዙ መጠየቅና መረዳት ያስፈልጋቹኋል ነውር ካለበት ክህንነት አትሥጡት እንደበተርቱ ዕም መሆን አለበት ካልሆነ ግን

በእዴሁ ተመጥዎ ሥጋሁ ወደሙ ለአንጊሌሁ ዓለም፡፡

28. ወለእመ ኮነ ሐንካሰ ዘኢይክል ሰጊረ ዘእንበለበትር ኢይኩን ካህነ ወለእመከህለ ሰጊረ ዘእንበለ በትር ይክል ይሰየም ይኩን ካህነ ዘሠናይ ግእዙ ለግብረ እግዚአብሔር ወቦቱ አእምሮ ወልቡና ወተርጉሞ መጻሕፍት ቅዱሳት ወያሴኒ ፍኖተ ቃሉ ዘበአማን መንፈሳዊት ወይመይጥ ሕዝቦ ውስተ ዘበአማን ፍኖተ ንሥሐ ከመ ይትዐረቁ ምስለ እግዚእነ ወአምላክነ ኢየሱስ ክርስቶስ፡፡

29. ወእመቦ እምሕዝብ ዕልዋነ ወመናፍቃነ እለ ጠምቁ ኢይሠየሙ በጉጉዓ እስከ ይትአመር ሑረቶሙ ተንቃቡ እምተዙላት እለያማስኑ አባግዓ መርዔቱ ለክርስቶስ፡፡

30. ኄርሰ ኖላዊ ይሜጡ ነፍሶ ቤዛ አበግዒሁ እግዚእነ ቤዘወነ አመ ይእሕዝዎ በይእቲ ሌሊት ወፌቀዱ የአሐዙነ ለነኒ ወይቤሎሙ ሕድግዎሙ ለእሉ እስመ ኪያየ ተሐስሱ

31. ወአንሰ ድኩም አፈድፈድኩ ተሐልፎተ ቃልየ ወእቤ አንሰ ኢይክሕደከ እመውት ምስሌከ ለዘቤዘወነ በነፍሱ ንህነ አባግዓመርዔቱ እለ ሀሎነ ምስሌሁ ቤዘወነ በደሙ፡፡

እንዴት ያስተምራል ለምዓምንም ለክህነት አትመድቡ ሥጋወደሙን የሚቀበሉ ሕዝብ የመፀየፍ ሁኔታ እንዳያሳዩ

28. አንድ እግሩ በሽተኛ ከሆነና ያለበትር መራመድ የማይችል ከሆነ ለክህነት አይገባም ያለበትር መራመድ የሚችል ከሆነ ግን ከክህነት አይከለከልም ካህን መልካም አንደበትና መልካም ተግባር ያለው ይሁን አዋቂና የሰከነ ዕውቀት ኑሮት ቅዱሳት መጻሕፍትን መተርጎም መቻል አለበት መንፈሳዊ ሕይወቱንም አሟልቶ መምራት የሚችል ይሁን ሕዝበክርስቲያን በንሥሐ ከጌታችን መድሐኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ጋር እንዲታረቁ የማድረግ ሐላፊነት የካህን ነውና፡፡

29. ከሕዝብ መካከል ከሐዲዎችና መናፍቃን ጥምቀትን ቢቀበሉ ትምህርትን እያገኙ ይቆዩ የቤተክርስቲያንን ሐላፊነት አይቀበሉ ይህ ከሆነ ማንነታቸው ሲጠና ሊረጋገጥ ይችላል የክርስቶስን በጎች ከሚነጥቁ ተኩላዎችም ተጠበቁ

30. መልካም እረኛ ስለበጎቹ ነፍሱን አሳልፎ ይሠጣል ጌታችን እኛ እንዳንያዝ እነሱን ተዋቸው ይሂዱ እኔ አለሁላችሁ ብሎ ስለኛ ራሱን አሳልፎ ሠጠ፡፡

31. እኔ ጴጥሮስ ደካማ ነበርኩ የቃል እላፊም አዘወትር ነበር ጌታችንን እኔ አልክድህም አልኩት ካንተ ጋርም እሞታለሁ አልኩት ይህንን ያልኩት የኢየሱስ ክርስቶስ መንጋዎች ሁነን ከሱ ጋር በነበርን ጊዜ ነው፡፡ እሱም በደሙ አዳነን፡፡

32. ውእቱሰ ተጠብሐ በእንቲአነ ወበእንተ ኵሎሙ ኃጥአን ከመ በግዕ ዘአልቦ ነውር ወኢከሠተ ሕማሙ በአፉሁ ከመ ያድሕነነ እምተኩላ መሣጢ ንሕነኒ ይደልወነ ንመጡ ነፍስነ ቤዛአባግዒነ እለ እምታሕቴነ ወኢንመጥዎሙ ለተኩላት መሠጥ።

33. አላ ናሠንዮሙ በኵሉ ምግባረ ሠናይ እንዘ ናመዕእሙ ኀቤሁ ወይዕቀቡ ሥርዓታ ለቅድስት ደብተራ ወይተአቀቡ እምትእይርቶሙ ለአቤሴላውያን ትውልደ ዓላውያን ወዓማፅያን እለቀነዮሙ አብሲስ ወመሀሮሙ ኵሎ ምግባረ እከይ ይትቃረንዋ ለቅድስት ቤተክርስቲያን እንዚያመዕኡ ኃእዘ።

34. ወእመቦ እምክርስቲያን ዘተአደወ ዘንተ ቀኖና ወአበየ እምዘአዘዝዎ ጳጳሳት ወቀሳውስት ኢይትኄለቍ ምስለ አባግዓ መርዔቱ ለክርስቶስ ይትከላእ እምቤተ ክርስቲያን መጠነ አዘዝዎ ካህናት ወሊቃነ ካህናት ወያግብዕ ካዕበተ ዘዓመፀ ዕዳሁ እምግብራ ለቅድስት ቤተክርስቲያን።

35. አመቦ እምጳጳሳት ወቀሳውስት ወዲያቆናት እለቀሠው እምንዋየ ቤተክርስቲያን እመሂ እምስምዕ ወቅብዕ ይርከቡ ተግሣፀ ወኵነኔ መጠነ ቀሠጡ እመቦ እምኔሆሙ ዘወለደ እምኔሆሙ እምውሉደ ዘሙት ወተግህደ ኀጢአቱ ይትመተር እምአርጊሁ ወእመሂ ብእሲተ ብእሲ ሆረ

32. እሱ ግን ስለኛ በግዓመሥዋዕት ሆነ ስለሌሎችም ሐጢአተኞች ቤዛ ሆነ ነውር የሌለበት የበግ ጠቦትም ሁኖ ስለኛ ሞተ። ከተኩላም እኛን ለማዳን እንደበቱን ከፈተ እኛም ከኛ በታች ሁነው እንድንጠብቃቸው ስለተሠጡን በጎች ነፍሳችንን እንስጥ ለተኩላዎች አሳልፈን አንስጣቸው።

33. ትተናቸው ሳንሸሽ ወጥተን ወርደን በማስተማር ወደእግዚአብሔር እናምጣቸው የቅድስት ደብተራንም ሥርዓት ጠብቁ አብሲስ የተባለው መናፍቅ ተነስቶ ክርክርን እያነሱ ቤተክርስቲያንን በመቃወም የሚሠለፉ ብዙ ተከታዩችን ወስዷል የሱ ተከታዮች የክህደትና የዓመፅ ሰዎች ናቸው ስለዚህ ከነሱ ተንከል ተጠበቁ

34. ክርስቲያኖች ሁነው ሳለ ይህን ከዚህ በላይ የታዘዘውን የማይፈፅሙ ካሉ ጳጳሳትና ካህናት ከስንፍና የተነሳ የማይፈፅም ካለ የታዘዘውን ሁሉ እስኪፈፅም ድረስ ከቤተክርስቲያን ይከልከል በስንፍና ያባከነውንም ገንዘብንም ሆነ ጊዜ በእጥፍ ይመልስ።

35. ከጳጳሳት ከቀሳውስት ከዲቆናት መካከል የቤተክርስቲያንን ንብረት የሠረቀ ቢገኝ የሠረቀውም ከቅብዕና ከሰም (ከጧፍ) ወይም ሌላ ይህን የመሰለ ቢሆን የቤተክርስቲያን መምህራን በሚሠጡት ውሳኔ የሚገባውን ቅጣት ያግኝ ከነሱ መካከል ከአመንዝራ ሴቶች ልጅን ቢወልድ ከቤተክርስቲያን ተወግዞ ይባረር ወይም የወንድን

ይትመተር እመዓርጊሁ

36. ኩሉ ብእሲ ይኅበር በብእሲቱ ወኵላ ብእሲት ትኅበር በምታ እስመ ዝንቱ ውእቱ ግብረ ማሕበሩ ለቅድስት ቤተክርስቲያን።

37. ወእመኒ ብእሲት ሐረት ኀበ ካልእ ይህድጋ ብእሲሃ ወትኅበር መበለተ እስከ ትፌፅም ንስሐሃ ወእመሰ ኢፈቀደ ሐዲጎታ ፂሆሙ ሐደግዎ ለእግዚአብሔር ወይትፈለጡ እምቤተክርስቲያን እስከይፌፅሙ ንስሐሆሙ

38. ወሶበፈፀሙ ንስሐሆሙ ወተመይጡ ውስተ ዘበአማን ንስሐሆሙ እምዕፁብ ይትወከፍዎሙ ወለእመሰ ካህናት ወዲያቆናት ተመትሩ እመዓርጊሆሙ ካህናት ብሂል እለይኔፅፉ ምሥጢሮ ለእግዚአብሔር።

39. ውእቱኒ ይነብር ማእከሌሆሙ እስመ አዕይንቲሆሙ ይኔፅራ ኀበእግዚአብሔር በህሊናሆሙ ወዘሰ ይብል እንዘ ካህን ውእቱ ኢይሬእዮ ለእግዚአብሔር ኢይግባእ ውስተ ንሥሐሁ ወኢይኔፅሮ ለእግዚአብሔር እስመ ኢሰአለ ኀቤሁ ሥርየተ ኀጢአት።

40. በከመ ይቤ ኤልያስ ቴስቢያዊ ሕያው እግዚአብሔር ዘአነ ቆምኩ ቅድሜሁ ዮም። ለእሉኬ ኢተውህቦሙ ምሥጢረ

ሚስት ቢያማግጥ ይባረር።

36. ወንድ ሁሉ በሚስቱ ፀንቶ ይኑር ሴት ሁሏም በባልዋ ፀንታ ትኑር የቅድስት ቤተክርስቲያን ማሕበር ተግባር ይህ ነው።

37. ባለትዳር ሁና ሌላ ወንድን በማፍቀር ብታመነዝር ባልዋ ይፍታት ንስሐዋንም እስክትጨርስ ድረስ መበለት ሁና ትቆይ ሚስቱ ከሌላወንድ ጋር ማመንዘርዋን እያወቀ ሊፈታት ካልፈቀደ ሁለታቸው ከእግዚአብሔር ተለይተዋል ስለዚህ ንስሐቸውን እስኪጨርሱ ድረስ ሁለቱ ከቤተክርስቲያን ይለዩ።

38. ንስሐቸውን ጨርሰው ሲመለሱና ወደቀድመው ሕይወታቸው በመለሱም እንኳ ክትትል ያስፈልጋቸዋል ካህናት ሁነው ይህን ፈፅመው ቢገኙ ግን ባስቸኳይ ከክህነታቸው ይወገዱ ካህናት ማለት ሁልጊዜ በዓይነሕሊና እግዚአብሔርን የማየት ሥልጣን የተሠጣቸው ናቸው።

39. እግዚአብሔርም በካህናት መካከል ይኖራል ምክንያቱም የካህናት ዓይነሕሊና ሁልጊዜ ወደእግዚአብሔር እንደተመለከቱ ናቸውና እግዚአብሔርን በዓይነህሊና አላየውም የሚል ካለ የንስሐንም ምሥጢር አይረዳውም ከእግዚአብሔርም የሐጢአትን ሥርየት አይለምንም ስለዚህ እንደወጣ ይቅር።

40. ቴስቢያዊው ኤልያስ እኔ የቆምኩለት እግዚአብሔር ሕያው ነው እንዳለ ለነኤልያስ ለካህናት የተሠጠውን ምሥጢረ እግዚአብሔር

ቅዱስ ለክሙስ ተውህበክሙ ወጥእምክሙ ፀጋሁ አንትሙ ሠራዕያነ መንግሥቱ እለ ትሜግቡ ሕዝበ እንዘ ትሜህርዎሙ ሠናየ ምግባረ ወአኮ ዝሙተ።

41. ወእመሰ አንትሙ ትገብርዎ መኑ ይጌሥፀክሙ ወመኑ ያረትዕ ፍናዊክሙ በዲበ ምድር ባሕቱ በሰማያት ትትኴነኑ ወይፀንሐክሙ ነደእሳት አርትዑ ፍናዊክሙ ወገሥፁ አንስትያክሙ ከመይትገኃሣ እምኩሉ እኩይ ዘኢያሠምሮ ለእግዚአብሔር።

42. ወይኩና ለሊሆን ለእለከማሆን መምህራተ ወገሣዕያተ ወለእመኮና ኄራተ ይገሥፃ ፳ናግለ ንዑሳተ ወአዋልዲሆን ወአዲ ባእዳትኒ እለ የሐውራ በሕገ ቅድስት ቤተክርስቲን ለእመ ክህላ ይገሥጻሆን ወይሚጣሆን ውስተ ሠናይ ግእዝ።

43. ወእመሰ ይንግራ ለአምታቲሆን ከመ እሙንቱ ያቁምዎን እምቤተክርስቲያን ገሥፁ ቢጻክሙ ኵሎ ጊዜ ወኵኑ ቀናእያነ ለጽድቅ ወለምግባረ ሠናይ እምንእስክሙ እስከ ዓቢይክሙ ከመይቤ ሐዋርያ ቅንዑ ለእንተ ተዐቢ ጸጋ አንስትኒ እለቦን አእምሮ ይገሥፃ አብያዊሆን ከመ ያድሕናሆን እም እኩይ።

44. በከመ ሐና ነቢዪት ወለተ ፋኑኤል ትሴብሖ

አልተሠጣቸውም ለናንተ ለካህናት ግን ምሥጢረእግዚአብሔርን የመፈፀም ዕድል ተሠጥቶአቹኋል እናንተም ፀጋውን ቀምሳችሁታል እናንተ ሕዝቡን የምትመግቡ ከዝሙትም እንዲርቁ የምታስተምሩ ናችሁ።

41. እናንተ ካህናት ሁናችሁ በኃጢአት ማጥ ውስጥ ከተዘፈቃችሁ እናንተን ማን ያስተምራል ማንስ ይገሥፃል በዚች ምድር ከናንተበላይማንም የለም ገሀነመእሳት ይጠብቃቹኋል መንገዳችሁን አስተካክሉ ሚስቶቻችሁም እግዚአብሔር ከማይገለገልበት መጥፎ ሥራ ሁሉ እንዲርቁ ገሥፁዋቸው።

42. እነሱ እንደነሱ ላሉት ሌሎች መሰሎቻቸው መምህር ይሁኑ የሚገሥፁም ይሁኑ ደግነታቸው የተስተካከለ ከሆነ ሌሎችን ሴቶች ደናግልንና የራሳቸውንም ሴቶች ልጆች ያስተምሩ ልጆቻቸውን ያልሆኑትንም በቤተክርስቲያን ህግ የሚሄዱ ልጃገረዶችን ወደመልካም መንገድ ለማስገባት ያስተምሩአቸው።

43. የነሱን ምክር ለመቀበል ፈቃደኛ ያልሆኑ ቢኖሩ ለባሎቻቸው ነግረው የቤተክርስቲያንን ቀኖና ያሠጡዋቸው። ክርስቲያን የሆናችሁ ሁሉ ለፅድቅ ቀናተኞች ሁኑ። ከትንሽነታችሁ እስከትልቅነታችሁ ከዚሁ አትራቁ ሐዋርያው ለትልቋ ፀጋ ቅኑ ብሏልና ዕውቀት ያላቸው ሴቶችም ባለንጀሮቻቸውን መክረው ከመጥፎ ሥራ ያስወግዱዋቸው።

44. ሴቶች የነቢዪቷ የፋኑኤል ልጅ ሐናን ፈለግ መከተል አለባቸው

ለእግዚአብሔር መዓልተ ወሌሊተ ወኢተዓርፍ ከናፍሪሃ ለጸሎት ወለባእድ። ወለባእድኒ ትምህርት ያድኅና እምዝሙት እመሂ ዘአውሰበት ብእሴ ወእመሂ ባእደ ይትቀነያ ለእግዚአብሔር በኩሉ ልቦን ወበኩሉ ምግባረ ሠናይ ዘያሠምሮ።

45. አንስት ወመንፈይምናት እለ ይእዜ ዮምኒ እግዚአብሔር ወአሜሃኒ እግዚአብሔር አሰንዩ ከመ ትትባልሁ ለእግዚአብሔር እምኩነኔሁ እእማቲከ እንዘ ድኩማት አቀብነ ትእዛዘከ ይእዜኒ ጕልቄነ ምስለ ቡሩካን አበግዒከ እለ እምቅደሜነ እግዚአብሔር ባርከነ አንትን እለ ዐቀብክን ሕሊናክን ወአንፃሕክን ሥጋክን በእንተ ፈሪሃ ስመዚአየ ዘየዐቢ ወይከብር።

46. ወእግዚእነ አዘዘነ እንዘይብል ዕቀቡ ትእዛዝየ ኢትፍልጡ አንስተ ወኢተባዕተ ኢአይሁዳዌ ኢገብረ ወኢአግአዜ ለእመ ተጠምቁ ወገብሩ ሠናየ ይትወከፍዎሙ ንሕነኒ ንብል ለእለይትለአኩ ሠናየ በንፁሕ ሥጋ በሰብሳቦን ወበድንግልናሆን ዘእንበለዘምዎ ትጉኒሂ ጳውሎስ ፀሐፈ በእንቲአሆን ወአመከሮን እንዘይብል እኤዝዞን በትእዛዘ ርእስየ አኮ ዘእም ኀበ እግዚአብሔር እግዚእየ።

47. ደናግል ወመዓስብ ለይትአገሳ ወለእመ ኢክህላ ተዓግሦ

ሓና ሴትተቀን ያለማቋረጥ እግዚአብሔርን ታመሰግን ነበር እንደበቷ ከፀሎትና እግዚአብሔርን ከማመስገን አያቋርጥም ነበር ሴትም ትሁን ያገባችም እግዚአብሔር ከዘማዊነት እንዲጠብቃት በሙሉ ልብ እግዚአብሔርን የምታገለግልበት መንገድ ትለምን

45. በመሐይምነት የተጠመዱ ሴቶች የዛሬውን በማስታወስ እግዚአብሔር የትናትና የዛሬ እሱ መሆኑን በመገንዘብ እግዚአብሔር እኛ ያንተባሮች ነን ደካማዎች ሁነን እያለ ትእዛዝህን ጠበቅን ስለዚህ ድካማችንን ተመልክተህ ከተቀደሱ በጎችህ ጋር ጨምረን እንድትሉትና እግዘአብሔርም እናንተ ሕሊናችሁን ጠብቃችሁ ሥጋችሁን ንፁሕ ያደረጋችሁ ናችሁ ይህንንም ስለከበረውና ታላቅ ስለሆነው ስሜነው እንዲላችሁ

46. ጌታችንም ስለሴቶች እንዲህ ሲል አዘናል ትእዛዜን ጠብቁ ሴትን ከወንድ አትለዩ አይሁዳዊ፣ አረማዊ ባርያ ጌታ ብላችሁ ልዩነትን አትፍጠሩ። ሁሉም ቅድስት ጥምቀትን ከተቀበሉ በኋላ በኔ ዘንድ አንድ ናቸው እኛም ይህንን መሠረት አድርገን ጋብቻቸውን አክብረው ለሚኖሩም ሆነ ድንግልናቸውን ጠብቀው ለሚኖሩ ሥርዓትን ሠርተናል ወንድማችን ጳውሎስም እኔ ለሴቶች ከእግዚአብሔር በተነገረኝ ሳይሆን ከራሴ እንዲህ እላቸውአለሁ አለና

47. ደናግልና መዓስባት በትዕግሥት ከዝሙት ተጠብቀው ይኑሩ

ያውስባ፣ እስመ ይኄይስ አውስቦ እምዘምዎ

48. እስመ እምንበ እግዚአብሔር አዙዝ ውእቱ ከመ ይዕቀባ ርእሶን ለአምታቲሆን።

49. አንቲ ገራሕት ዕቀቢ ርእሰኪ ወኢትደምሪ ዘርአ ነኪር እንዘ ሀሎ ዘይናዝዘኪ ሐዘንኪ ሶበ ከመዝ ዘርእኪ ቡሩክ ውእቱ።

50. እስመ እምእግዚአብሔር ኮነ ዝ ኵሉ አንትሙኒ ዕቀቡ ትእዛዞ ወአንብቡ ኵሎ ዘጽሑፍ በተጠናቅቆ ዘእንበለመጽሐፍ ወትምህርት አልቦ ዘተአምሩ ተመሐሩ እምሊቃናት ወአፅምዑ ቃለመጻሕፍት።

51. ደዩ ውስተ ልብክሙ ቃለ መለኮት ወኢትርስኡ ቃለመምህርክሙ ወአፍቅሩ ቢጸክሙ ከመነፍስክሙ እስመ መጽሐፍ ይቀትል ወመንፈስ የሐዩ። እስመ መፅሐፍ ኦሪት ወመንፈስ ወንጌል።

52. ሑሩ በፍኖተ ወንጌል ከመ ትሕየው ወዕቀቡ ሥርዓተ ቀኖና ከመ ትትመሐሩ ገቢረ ሠናይ ወፈቃዶ ለእግዚአብሐየር ወኢታስትቱ ሰሚዓ ቃለ መጻሕፍት ዘመለኮት ይትዓወቁ በቃሎሙ።

53. እስመ መጻሕፍት ዘመለኮት እምቃሉ ይትዐወቁ ወሐሳውያንሂ ዘኢኮኑ እምቃሎሙ ይትዐወቁ ወኢይቶስሑ

መታገሥ ካልቻሉ ግን ያግቡ ከዘማዊነት አግብቶ መኖር ይሻላልና።

48. ራሳቸውን ጠብቀው ይኖሩ ዘንድና ከባሎቻቸው ውጭ እንዳይሆኑ ታዟል።

49. አንቺ እርሻ ራስሽን ጠብቂ ሌላ ዘርን አትጨምሪ የሚያጽናናሽና ከሐዘንሽ የሚያረጋጋሽ ባልሽ ብቻ ነው።

50. ይህ ሁሉ ከእግዚአብሔር ዘንድ ሆነ እናንተም የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ጠብቁ የተጻፈውንም ሁሉ አንብቡ። በጥንቃቄም አስተውሉ ሳትማሩና መፃሕፍትን ሳታነቡ የምታገኙት እውቀት አይኖርም ከሊቃውንት ተማሩ የመፃሕፍትንም ቃል አድምጡ

51. የመለኮትን ቃል ከልባችሁ ውስጥ አስቡ የመምህራችሁ ቃልንም አትርሱ ባልንጀራችሁ እንደራሳችሁ ውደዱ መፅሐፍ ይገድላል መንፈስግን ያድናል መጽሐፍ የተባለው ኦሪት ነው መንፈስ የተባለው ግን ወንጌል ነው።

52. በወንጌል መንገድ ሂዱ። ትድኑ ዘንድ የቀኖናንም ሥርዓት ጠብቁ ከእግዚአብሔር ፈቃድ በተመሠረተ መልካም ሥራን ትማሩ ዘንድ የመፃሕፍትን ቃል ከመስማት ወደኋላ አትበሉ የመለኮት መጻሕፍት በቃላቸው ይታወቃሉ

53. የመለኮት መጻሕፍት ከቃላቸው ስለሚታወቁም የሐሰት መጻሕፍት ከነሱ ጋር እንዳይጨመሩ ቅድስት ቤተክርስቲያን

ትእዛዘ ለቅድስት ቤተክርስቲያን እስመ ነገር እኩይ ለእመቦአ ውስተ እዝን የሐብል ልበ ሠናየ።

54. ኢትኩኑ ንፉቃነ አላ ዕቀቡ ቀኖና ዘቅድስት ቤክርስቲያን ከመ ታድሕኑ ርእሰክሙ እምዝ ዓለም እኩይ እምቅድመ ይምጻእክሙ ሞት ያወርደክሙ ውስተ ሲኦል ለእመ ኢአቀብክሙ ሥርዓታ ለቅድስት ቤተክርስቲያን።

56. ተዐቀቡ እምስካር እንዘተበውኡ ውስቴታ። እስመ በቀዳሚት ሕግ እንተ ይእቲ ኦሪት አዘዞሙ ሙሴ ለሌዋውያን ኢይስክሩ አማሁ አንትሙኒ ኤጲስ ቆጶሳት ቀሳውስት ወዲያቆናት ተዓቀቡ እምስካር እስመ እምስካር ይመፅኡ ምርዓት ዝሙት፣ ስስዕት፣ ፅርፈት ትዕቢት ወመሐላ በሐሰት ወዝንጋዔ።

57. ተዐቀቡ እምስታየወይን ወስካር ወአፈድፍዱ ስትየ ቃለ እግዚአብሔር ወመጻሕፍት ዘመለኮት እስመኮልነ ሰተይነ አሐደ ሥጋ ወአሐደ መንፈሰ። በእንተዝ ኩልነ ንከውን አሐወ። ወአመ ንቀውም ቅድሜሁ ኩልነ ንትፌሣሕ ሕቡረ።

68. ዲያብሎስ ወአጋንንቲሁ ኢይፈቅዱ ይድሐን ፩ዱሂ እምሰብእ ለእመተክህሎሙ ለዘኢየአቀብ ትእዛዘ እግዚአብሔር ይቀንዮ

ታስጠንቅቃለች መጥፎ ነገር ካለና ከደሕና ነገር ከተጨመረ ጆሮላይም ከገባ መልካሙን ልብ ያደፈርሰዋል።

54. ተጠራጣሪዎች አትሁኑ የቅድስት ቤተክርስቲያንን ቀኖና ጠብቁ እንጂ ከዚህ ዓለም ካለው መጥፎ ሥራንም ራሳችሁን ጠብቁ ሞት ሳይመጣባችሁ ለመልካም ሥራ ተሽቀዳደሙ በክፉ ቦታ እያላችሁ ከሞታችሁ ወደሲኦል ትወርዳላችሁ ይህ ሁሉ የሚያገኛችሁ የቅድስት ቤተክርስቲያንን ሥርዓት ካልጠበቃችሁ ነው።

56. ከሥካር ተጠበቁ ሙሴ በኦሪት ለሌዋውያን እንዳይሠክሩ አዟቸዋል እንዲሁ እናንተ ኤጴስቆጶሳት ቀሳውስትና ዲያቆናት መጠጥን ከማብዛትና ከሥካር ተጠበቁ መዳራት፣ ዝሙት፣ ስግብግብነት ሰውን መስደብና ማስቀየም መታበይ፣ በሐሰት መማል፣ ብዙ ቁምነገሮችን መዘንጋትና ሌሎችም ከሥካር የሚመነጩ ናቸውና

57. ከሥካርና ወይንን ከማብዛት ተጠበቁ ቃለእግዚአብሔር የሠፈረባቸውን መጻህፍት መጠጣትን አዘውትሩ እንጂ ሁላችን አንድ ሥጋንና አንድ መንፈስን ጠጥተናል ስለዚህ በቤተክርስቲያን ሕግ መሠረት ከተጠበቅን በሕብረት ከጌታችን ፊት እንቆማለን

68. ዲያብሎስና ጭፍሮቹ ማንም ሰብአዊ ፍጡር እንዲድን አይፈልጉም ከተሳካላቸው ሁሉም ሰው እንዲጠፋ ነው

ሠይጣን

69. አዝዙዎሙ ለመንይምናን የንቡ ምዕዋተ እምዘበሙ እምዘርአ ቤቶሙ ከመ ይባርኮሙ እግዚአብሔር ወለእመቦ ሕጡዕ እምሲሳ የዕለቱ ያአንኪ ወያፍእም ለነዳይ እምይእቲ

70. ለእመ ገብረ ከመዝ እግዚአብሔር ያነብሮ ውስተ ርእሰ ሕዝብ በዝ ዓለም ወበዘይመጽእኒ ዓለም ምስለ ማሕበረ ቅዱሳን። ኢታስትቱ ገቢረሠናይ ከመ ትዕድው እሞት ውስተሕይወት ወኢትትሐወሉ ምስለ ዕልዋነ ሃይማኖት

71. አንትሙኒ ውሉደክርስቲያን ኢታስትቱ ገቢረ ዘንተ ነገረ ዘነገርናክሙ አዝዙ ሕዝበ ይግበሩ ዘሠራዕነ ለክሙ።

72. እመቦ ዘይቀውም ወኢይገብር እሞዘ ሠራዕነ ለክሙ ይኩን ውዱቀ እምአርጊሃ ለቅድስት ቤተክርስቲን

73. ዕቀቡ ሥርዓታ ለቅድስት ቤተ ክርስቲያን እንተ እግዚእነ ኢየሱስክርስቶስ ከመትኩኑ ውሉደ ለአቡክሙ ዘበሰማያት እስመ ውእቱ ኄር ለኄራን

74. እስመ ውእቱ ኄር ለኄራን ወኢይትሔየይ ለኃጥእ በእንተ ኃጢአተ ወኵሉ ሎቱ ወኵሉ እምኀቤሁ ወኵሉ በፈቃዱ ኵሉ ሥጡሕ ወክሱት። ዕቀቡ ሥርዓታቤተክርስቲያን

ፍላጎታቸው።

69. መሐይምናን ካላቸው ንብረት ለድሆችም ምዕዋትን ይሠጡ ዘንድ እዘዛቸው ይህን ካደረጉ እግዚአብሔር ይባርካቸዋል። ምንም የሌለው ድሐ ቢሆን እንኳ ካለችው የዕለት ጉርሱ ከፍሎ ይመፅውት

70. ይህን ከፈፀመ እግዚአብሔር በዚህ ዓለም እያለ ካለበት ደረጃ ከፍ ያደርገዋል በወድያኛው ዓለምም ከማሕበረቅዱሳን ጋር ይጨምረዋል ከሞት ወደሕይወት ለመሻገር ትችሉ ዘንድ መልካም ሥራን ችላ አትበሉ ከዕልዋን ጋርም አትቀላቀሉ።

71. እናንተ የክርስቲያን ልጆች የነገርናችሁን ነገር ወደኋላ ችላ አትበሉ። ሕዝቦቹ ለናንተ የሠጠነውን ሥርዓት ጠብቀው ይኖሩ ዘንድ እዘዙዋቸው

72. ይህንን የሠጠናችሁን ሥርዓት የማይቀበልና የማይመራበት ሰው ካለ ከቅድስት ቤተክርስቲያን መዓርጉ ይወድቃል።

73. የቤተክርስቲያንን ሥርዓት ጠብቁ እሷ የጌታችን መድሐኒታችን ኢየሱስክርስቶስ ናትና ይህንን ማድረጋችሁ በሰማያት ላለው አባታችሁ ልጆች እንድትሆኑ ነው። እሱ ለደግ ሰዎች ደገኛ አምላክ ነውና

74. እግዚአብሔር ለደገኞች ደግ ነው ሐጢአተኛን ስለሐጢያቱ ችላ አይለውም ሁሉ ለሱ ነው ሁሉም ከሱ ዘንድ ነው ሁሉ በፈቃዱ ይሆናል ሁሉ ከፊቱ ተዘርግቶ ይታያል ሁሉም ከሱ ዘንድ ግልፅ

ወኢትትገሐሱ እምኔሃ ከመትኩኑ ፍሡሐነ በበአትክሙ ወበፀአትክሙ ውስቴታ።

75. እስመ ለነ ለአሠርቱ ወ፪ሐዋርያት አዘዘነ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ከመ ንሥራዕ ሕዝበ በጽድቅ ወበርትዕ ወኢናድሉ ለገፀ ሰብእ አላ በከመቀኖና ዘቤተክርስቲያን ይደልዎ ቁመት ወምሕረት ወኢነሀብ ለሕዝብ ካልአ ምክንያተ በዘይትገሐሱ እም ሥርዓታ ለቤተክርስቲያን።

76. እስመሀለው በምክንያት እለይትገሐሱ እምሥርዓተ ቤተክርስቲያን እንዘ ይብሉ ለነሰ አዘዙነ ሥዩማኒነ ከመ ንግበር ፈቃዶሙ ለእለይመልኩ ዓለመ ወኢንክል ተጠናቅቆ ውስተ ሥርዓተ ቤተክርስቲያን።

77. እንበይነዝ ኢያሰነዩ ሥርዓቶ ለእግዚአብሔር ወእግዚአብሔርኒ ይወቅሶሙ

78. እስመ ነገሥት ወመኳንንት ርቱዓ ይትአዘዙ ለእግዚአብሔር በእንተ ነፍሶሙ።

78. እስመ ይኄይስ አሰንዮ ነፍስ እምነ ሥጋ እስመ እለ ዘሥጋ ይሄልዩ ይፈቅዱ ያድልው ለሰብእ ወእለሰ ይፈቅዱ ያድልው ለእግዚአብሔር እሙንቱ ኢየንጥኡ ዘሥጋ ወዘነፍስ።

79. እስመ ለሊሁ ይሜህሮሙ ከመያድልው ሎቱ በከመፈቀዱ

ነው። የቤተክርስቲያንን ሥርዓት ጠብቁ ከሷም አትራቁ ከሷ ካልራቃችሁ ስትወጡና ስትገቡ ፍፁም ደስታ ይሰማቹኋል።

75. ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ለኛ ለአሥራሁለት ሐዋርያት ሕዝቦቹን በእውነትና በቅንነት እንመራ ዘንድ አዞናል በቤተክርስቲያን ቀኖና መሠረት እንጂ በሌላ ምክንያት ለሰው ፊት በማዳላት ቅጣትንም ሆነ ሌላ በሰው ላይ እንዳናስተላልፍም አዞናል ስለዚህ ከቤተክርስቲያን ቀኖናና ሥርዓት ውጭ በሆነ መንገድ ሕዝቦችን አንቀጣም።

76. በሌላ ምክንያት ከቤተክርስቲያን ቀኖና የሚወጡ አሉ የምድር ገገርዎች ፈቃዳቸውን እንፈፅም ዘንድ ሌላ ትእዛዝ ያዙናል የቤተክርስቲያንን ሥርዓት በጥንቃቄ ልንከታተል አንችልም በማለት ብዙ የተለያየ ምክንያት ያቀርባሉ

77. ይህንንም ምክንያት መነሻ እያደረጉ የእግዚአብሔርን ሥርዓት ችላ ይላሉ እግዚአብሔርም ይወቅሳቸዋል

78. ነገሥታትና መኳንንት በቤተክርስቲያን እንደማንም ተራዎች ናቸው ስለዚህ ስለነፍሳቸው በትክክል የቤተክርስቲያንን ሥርዓት ይጠብቁ

78. ለሥጋ ከማድላት ለዘዓለማዊቷ ነፍስ ማድላት ይሻላል ለስጋ ብቻ የሚያስቡ ለሰው እንዲያደሉ በራሳቸው ይገደዳሉ ለእግዚአብሔር ማድላትን የመረጡ ግን በረከተነፍስንና በረከተሥጋን አያጡም

79. እግዚአብሔር ራሱ በቀና መንገድ እንዲጓዙ ይመራቸዋል

ወይመርሐሙ ውስተ ገቢረ ትእዛዛቲሁ እግዚአብሔር፡፡

80. እመቦ ዘተግሕሰ እምሥርዓተቤተክርስቲያን ወሐብሩ ላእሌሁ ሊቃናተ ቤተክርስቲያን ወሰከዩዎ በሕገዓመፃ ወውእቱ ኢተግህሰ እስከይፈትሑ ቦቱ ሊቃናተ ቤተክርስቲያን አላ ኮነ ምሕዉነ ኀበ መኳንንተዓለም ወአበየ ተግሕሶ እምዘ ግእዝዎ፡፡

81. ውእቱኬ ይከውን ቅውመ እምቤተ ክርስቲያን ወኢይደመር ምስለ ሕዝብ እስከ አመይኔሥሕ ወአልቦ ዳግም ሰ[illegible]ት ኀበ ሊቀጳጳሳት፡፡

82. እመቦ እም ሕዝበውያን ወእም ካህናት ዘይትዌከፍ ውጉዘ ቅውም ውእቱ እምቤተክርስቲያን ወይትወገዝ ምስለ ዘተወክፎ ዓማፂ

83. ይደሉ ለካህናት ይትወከፉ ኀጥአነ ለንሥሐ ዘእንበለ አድልዎ ወኢይትወከፉ ሕልያነ እም ተነሳሕያን ለአቅልሎ ንሥሐ አላ የሀቡ ንሥሐ ዘእንበለ አድልዎ ወለእመሰኬ መምለኬ ጣዖት ያክብዱ ንሥሐሁ እስመ እምኵሉ ኀጢአት የአኪ አምልኮ ጣዖት በኀበእግዚአብሔር

84. ዕቀቡ ሥርዓተ ቀኖና ዘተውህበ ለመሐይምናን ሕዝበ ክርስቲያን እለሖሩ በምግባረ ሠናይ ወአሕለፉ መዋዕሊሆሙ

ወደሱም ዝንባሌአቸው እንዲሆን ያደርጋቸዋል የሱንም ትእዛዛት ጠብቀው እንዲኖሩ ያደርጋቸዋል

80. የቤተክርስቲያንን ሥርዓት አፍርሶ የክርስቲያን ዓለቆች ጥፋቱን በመመልከት ጥፋተኛ ሆኖ ስላገኙት ቢቀጡትና የነሱንም የቅጣት ውሳኔ ለመቀበል ፈቃደኛ ሳይሆን ቀርቶ ወደሥጋውያን ዳኞች በመሄድ የቤተክርስቲንን አለቆች ቢከስና ከቤተክርስቲያን ቀኖና ውጭ ቢሆን

81. ይህን የመሰለ በደለኛ ከቤተክርስቲያን መራቅ ይገባዋል ከማሕበረምእመናን ጋርም አይካፈልም ንሥሓውን ሲጨርስ ካልሆነ በቀር ወደቤተክርስቲያን እንዲገባ አይፈቀድለትም

82. ከካህናትና ከሕዝባውያን መካከል የተወገዘውን ሰው ተቀብሎ ቢገኝ ከተወገዘው ሰው ጋር ከቤተክርስቲያን ተለይቶና ተወግዞ ይባረር

83. ለካህናት ሐጢአተኞችን ለንሥሐ ያለአድልዎ መቀበል ይገባል ንሥሐን እናቀልልሃለን ብለው ከተነሣሂ መማለጃን አይቀበሉ፡፡ ይልቁንስ የሐጢአቱን ክብደትና ብዛት በመመልከት ተገቢውን መንፈሳዊቅጣት ይሥጡት ጣኦትአምላኪ ከሆነ ንሥሐውን ያክብዱበት በእግዚአብሔር ዘንድ ከባዱ ሐጢአት ጣዖትን ማምለክ ነውና፡፡

84. በመልካም ምግባረሠናይ የሚኖሩትንና መላ ሕይወታቸው ለፅድቅ ሥራ ለሚያውሉ መሐይምናን ሕዝበክርስቲያን

በምግባረ ጽድቅ ወበንስሐ ከመ ይትፌሥሑ ለዝሉፉ እስከለዓለም በኢየሱስክርስቶስ ዘአድኀኖሙ በደሙ።

85. አመ ተሰቅለ ክርስቶስ ተረግዘ ገቦሁ ወእምኔሁ ውሕዘ ደም ወማይ ወበማይ ዘውሕዘ እምገቦሁ ቀደሳ ለቤተ ክርስቲያን ከመ ትኩን ምሥትሥራየኀጢአት። እስመ ይእቲ እምነ እንተ በሰማያት አግአዚት።

86. ወነፍስ ክርስቲያን ይእቲ መርዓተ ቤተክርስቲያን ወኢይትኌለቁ ውስተ መርዔታ እለ ገብሩ አበሳ ወሖሩ ዘእንበለ ሕግ ወእለ ይመይጡ ዓይኖሙ ኀበ ብእሲተባእድ ከመ ያስሕቱ።

87. እለ ይገብሩ ሰገለ ወጣዖተ ውስተቤቶሙ ወይገብሩ ዝሙተ ወተውኔተ በቤቶሙ ወውዓ ወእለ ኢያፈቅሩ ነግደ ወእንለማውታ ወእለአጽደቁ ርእሶሙ በከንቱ ወይሜንኑ ቢያሙ ውፁአን ወግዑዛን፣ ወግሑሳን እምሕገ ቀኖና ቅድስት ቤተክርስቲያን

88. እለ ከመዝ ውዱቃን ሰብእ እምተምሕሮ ወንጌል ለእመ ሐደጉ እኩየ ግብሮሙ ወነስሁ ይግብኡ ኀበ ዘቀዳሚ መዓርጊሆሙ። እስመ ብክሙ አእምሮ ገበሩ በዘይደሉ።

የተሠጠውን ቀኖና ጠብቁ እነሱ በንሥሀ ሕይወታቸውን ከዳኗ በደሙ ካዳናቸው ጌታችንና መድሐኒታችን ኢየሱስክርስቶስ ጋር ሁነው እስከዘለዓለሙ ይደሰታሉ

85. ክርስቶስ በተሠቀለ ጊዜ ጎድኑ በጦር ተወጋና ከጎድኑ ደምና ውኃ ፈሰሰ በዚሁ ውኃ ክርስቲያኖች ይጠመቃሉ። ቤተክርስቲያንንም በደሙ ቀድሷታል የሐጢአት ማስተሥሪያ ትሆን ዘንድ እሷ እኛን ነፃ አውጥታ በሰማያት እናታችን ትሆናለችና።

86. የክርስቲያን ነፍስ የቤተክርስቲያን ሙሽራ ናት ነገር ግን ዓይናቸውን ወደሌላ ሴት የሚያዞሩና ሌሎችንም ለማሳሳት የሚሯሯጡ ሁሉ በደለኞች ስለሆኑ ከቤተክርስቲያን መንጋዎች አይቆጠሩም

87. ጥንቆላን በቤታቸው የሚያካሂዱ ጣዖትንም የሚያመልኩ ዝሙትን የሚያፈቅሩ በቤታቸው ጭፈራንና ዳንኪራን የሚያዘወትሩ እንግዳን መቀበልና የሙትን ልጆችን መርዳት የማይፈልጉ ራስወዳዶች የሆኑ ባለንጀራቸውንም የሚንቁ ከህገቀኖና ቤተክርስቲያን የወጡና ፈፅመው የተለዩ ስለሆኑ ማንም ክርስቲያን ሊመስላቸው አይገባም

88. ከላይ በተጠቀሱ የሐጢአት ዓይነቶች የወደቁ ሁሉ በንሥሐ ከተመለሱ ቅዱስ ወንጌልንም ከመማር የተነሳ መጥፎሥራቸውን ሁሉ ትተው በቅድስት ቤተክርስቲያን ውስጥ የነበራቸውን የቀድሞ ክብራቸው እንዲይዙ አድርጉ።

89. ለዘ ትፈቅዱ አናሕስዬ ሎሙ ወለዘትፈቅዱ ትገሥፁ ገሥፁ ወለዘ ተመትረ እመዓ ርገቤተ ክርስቲን ምትሩ። በከመ ብዝሐ አበሳሆሙ አክብዱ ንሥሐሆሙ ወበከመ ውሑድ አበሳሆሙ አቅልሉ ንሰሐሆሙ።

90. ከመ ይትፈሳሕ እግዚአብሔር ብክሙ እስመ ሰብአ ምሕረት እሙንቱ ደቂቃ ለቤተ ክርስቲያን ወኢትጠናቀቁ ላእለ እኩይ ለአስተፍስሖ ቢጽክሙ ወኢታስተሐቅርዎሙ ለንኡሳን እለቦሙ አእምሮ።

91. ወአኮ ለአረጋዊያን ባህቲቶሙ እለቦሙ አእምሮ ወለካልእኒ ይቤ አኮ ለዘጐንደየ መዋዕሊሁ ወለዘየዓቢ ሥርዓተ ወፈቲንከ ልቦሙ ወአእምሮቶሙ አዝዞሙ ይገሥፅዎሙ ለሕዝብ።

92. ለእመ መፅኡ ኀቤሁ በጥቡዕ ልብ የአዝዝዎሙ ከመ ኢይግብኡ ኀበ ዘቀዳሚ ኀጢአቶሙ ኩንዎሙ አርአያ ለሕዝብ እለይፈቅዱ ያድሕኑ ርእሶሙ በትምሕርተ ዚአክሙ ወበሠናይ ትምህርት መንፈሳዊት እንተ ታበፅሕ ኀበ እግዚአብሔር በብሩህ ገጽ። ከመ ይትፈሳሕ ባቲ ምስለ ጻድቃን።

89. ትራሩለት የፈለጋችሁት ሰው ካለ ራሩለት ልትገሥፁት የምትፈልጉት ካለ ገሥፁት ከቤተክርስቲያን ልጅነት እንዲወገድ የምትፈልጉት ካለ አስወግዱት ብዙ ጥፋት ለፈፀመ እንደጥፋታቸው መጠን ንሥሐ ሥጡዋቸው በደላቸው ጥቂት ለሆነ ጥቂት ንሥሐ ስጡዋቸው።

90. ይህንን ከፈፀማችሁ እግዚአብሔር ደስ ይለዋል የቤተክርስቲያን ልጆች የርሕራሄና የይቅርታ ሰዎች ናቸው ክፉ ሥራ የሚሠራውን ሰው ወደእግዚአብሔር ከተመለሰ ስለፈፀመው ሐጢአቱ ቁጥጥርን አታብዙበት እውቀት ያላቸውን ሰዎች ደግሞ በትንሽነታቸው ችላ አትበሉዋቸው።

92. አዋቂዎች ለመሆን የሚችሉ አረጋውያን ብቻ አይደሉ ም በዕድሜ ሳይገፉም ጥሩ መንፈሳውን የሚሆኑ አሉ፣ በዕድሜ መግፋት ብቻ ወይም ብዙ ዓመታትን በመኖር ብቻ ለትልቅነት አይደረስም ሰዎችን የውስጥ ሕይወታቸውን በመመርመር ህዝብን እንዲመሩ እዘዛቸው።

92. ጥብዐት በተሞላበት አኳኋን ሰዎች ወደ እግዚአብሔር ከመጡ ወደቀድሞው የሐጢአት ቦታቸው እንዳይመለሱ ካህናት ይጠብቁዋቸው እናንተም ራሳቸውን ከሐጢአት ለማዳን ለመጡት መልካም አርአያነትን ሥጡዋቸው በመልካም መንፈስዊ ትምህርትም እንዲታነፁ አድርጉ መልካም መንፈሳዊ ትምህርት በበራ ገፅ ወደእግዚአብሔር ታደርሳለች በዚሁ ትምህርት የታነፁ

93. ኢትሑሩ በምክረረሲዓን ወሐጥአን እለኢያፈቅርዎ ለንሥሐ በዲበምድር እሙንቱ ይብሉ ንብላዕ ወንሥተይ እስመ ጌሰመ ንመውት ወኢነአምር ዘይከውን ሙታን ወእመኣከ ይትነሥኡ ባሕቱ ይከውኑ ሐመደ እምነዋሕ መዋዕል ወለእመቦኡ ፻፻ ሰብእ ውስተ ፩ መቃብር ለይትረከብ ምልአ እድ ሐመደ፡፡

94. በዝ ይስሕቱ ለሊሆሙ ወያስሕቱ አብያጊሆሙ ወይወስድዎሙ ውስተኵነኔ ባሕቱ እግዚአብሔር ኢያደሉ ለገጽ አላ በኵነኔ ጽድቁ የአሲ ለኵሉ፡፡

95. እስመ ከመ ይትነሥኡ ሙታን ነገሮ እግዚአብሔር ለሙሴ በነበዕፀጳጦስ ወይቤሎ ኢኮንኩ አምላከ ሙታን አላ አምላከ ሕያዋን እስመኢኮኑ ምውታነ በኀቤሁ ጻድቃን ዳእሙ ሕያዋን እስመኀጥአን ዳግመ ይመውቱ ጻድቃንሰ ዳግመ ኢይመውቱ አላ ይፀንሖሙ ሕይወት እስመ ይተፌሥሑ ወትረ ምስሌሁ በመንግሥተ ሰማያት፡፡

96. ኀጥአን እሙኒ ሕያዋን በሥጋሆሙ ምውታን በነፍሶሙ በቅድመ እግዚአብሔር አዳም አቡነ እንዘሃሎ በነፍሱ ወሥጋሁ ውስተ ገነት ኮነ ሕያወ ወይትናዘዝ ምስለ

ምእመናንም ከቅዱሳን ፃድቃን ጋር ይደሰታሉ፡፡

93. በግድየለሾችና በሐጢአተኞች መንገድ አትሂዱ እነሱ ንሥሐን አይወዱም በዚች ምድር እያሉ ነገ እንሞታለንና በሕይወት እያለን እንብላ እንጠጣ ይላሉ ስለሙታን መነሳትም እምነት የላቸውም የሞተ ሰው ሁሉ የሚጠብበው መቃብር ውስጥ አመድ ሆኖ መቅረት ብቻ ነው ከጊዜ ብዛት የሰው አካል በመቃብር ውስጥ ጥሪኝ አመድ ይሆናል በእልፍ የሚቆጠር የሰው አካል ባንድ መቃብር ቢቀበር እጅ የሚሞላ አመድ አይገኝም ይላሉ

94. በዚሁ ሁሉ ይስታሉ ባለንጀሮቻቸውንም ያስታሉ ወደኩነኔም ይመሩዋቸዋል እግዚአብሔር ግን የሰውን ፊት እይቶ አያዳላም በእውነታው ፍርዱ ሁሉን እንደየ ሥራው ይከፍለዋል እንጂ

95. ሙታን ደግሞ እንደሚነሱ ለሙሴ በዕፀጳጦስ እግዚአብሔር በተናገረው ቃል ተገልጿል የሕይያዋን አምላክ ነኝ እንጂ የሙታን አምላክ አይደለሁም ብሎታልና ጻድቃን በእግዚአብሔር ዘንድ ሕያዋን እንጂ ሙታን አይደሉም ሐጥአን ዳግም ሞት ይጠብቃቸዋል ጻድቃን ግን ዳግም ሞት አይጠብቃቸውም ሕይወት ይጠብቃቸዋልና በመንግሥተሰማያትም ከእግዚአብሔር ጋር ሲደሰቱ ይኖራሉ

96. ሐጢአተኞች በዚህ ዓለም እያሉም በነፍሳቸው የሞቱ ናቸው (በእግዚአብሔር ፊት) አዳም በገነት እያለ በነፍሱም በሥጋውም ሕያው ነበር ከመላእክት ጋርም ይነጋገር ነበር አውሬዎች

መላእክት ወይመፅኡ አራዊት ወይሰግዱ ሎቱ ወአዕዋፈ ሰማይ ይትኤዘዙ ሎቱ ወአመ [illegible] በነፍሱ

97. ወመላእክት እለይትናዘዙ ምስሌሁ ሰደድዎ እምውስተገነት አፍአ አራዊት ወአዕፍ ኮንዎ ፀረ ወኮኑ እለይበልዑ ሥጋሁ ወኢተአዘዝዎ

98. ወከማሁ ኵሎሙ ኃጥአን እለይገብሩ ኀጢአተ እምድሕረ ጥምቀት ምውታን በነፍሶሙ እንዘ ሕያዋን በሥጋሆሙ በዲበምድር። አንትሙ አሙቱ ሥጋክሙ እምዝሙት ወአህይው ነፍስክሙ ለእግዚአብሔር በምግባረ ሠናይ ወጽድቅ።

99. ካዕበ አሙቱ ነፍስክሙ በዝ እምኩሉ እኩይ ወርሱሕ ዘኢያሠምሮ ለእግዚአብሔር ወአሕይው ነፍስክሙ ወሥጋክሙ ወተፀመዱ ለቤተክርስቲያን ከመ ትዕድው እሞት ውስተ ሕይወት

100. አነ ጴጥሮስ ርእሰ ሐዋርያት አበ መንፈስክሙ ወአኮ በሥጋ አላ አዛዚ በመንፈስ ዘወሀበኒ አምላኪየ አነ መምሕርክሙ ወሀብክዎ ለቀሌሚንጦስ ወልድየ ከመ የአዝዞሙ ለእለ በሙ አእምሮ ወኢይትከሰት ሎሙ ለእለ አልቦሙ አእምሮ ከመ ኢይኩን ነገርየ ሥላቀ በኀቤሆሙ።

ይሰግዱለት ነበር የሰማይ ወፎችም ይታዘዙት ነበር የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ካፈረሰ በኋላ ግን በነፍሱ ሞተ

97. ያረጋጉትና ያጫውቱት የነበሩት መላእክት ያሳድዱት ጀመር ከገነትም አስወጡት አውሬዎችና ወፎች ጠላቶቹ ሆኑ ሥጋውንም ለመብላት ፈለጉ የማይታዘዙትም ሆኑ

98. እንደዚሁ ሐጢአተኞች በሙሉ ከጥምቀት በኋላ ሐጢአትን በመሥራታቸው በነፍሳቸው የሞቱ ናቸው በአካለሥጋ እያሉ እናንተ ይህንን ሁሉ እያስተዋላችሁ ሥጋችሁን ግደሉ እንጂ ነፍሳችሁን አትግደሉ ከዝሙትም በመጠበቅ የእግዚአብሔር ቤተሰቦች ሁኑ ነፍሳችሁንም በእውነትና በመልካም ሥራ ለእግዚአብሔር አገልግሎት ዝግጁዎች ሁኑ

99. ዳግመኛም ነፍሳችሁንም እግዚአብሔርን ከማገልገል አታርቁ ከነፍስ ጉስቁልናም ሁሉ ከክፋትም ሁሉ ራቁ ነፍሳችሁንና ሥጋችሁን አድኑ ከሞት ወደሕይወት ለመሸጋገር እንድትችሉም ቤተክርስቲያንን በትክክል አገልግሉ።

100. እኔ የሐዋርያት አለቃ ጴጥሮስ በሥጋ እያላችሁ ነፍስ አባታችሁ ነኝ ይህንንም ሥልጣን የተረከብኩት ከአምላኬ ነው። የማዘዝ ሥልጣን ለኔ ተሠጥቷል እኔም ይህን ትእዛዝ ሁሉ ለልጄ ቀሌሚንጦስ አስረከብኩት ቀሌሚንጦስ በበኩሉ ለመስማትና ከሐጢአት ለመመለስ ዝግጁዎች የሆኑትን ሁሉ በዚሁ መንገድ ያስተምራቸዋል ለመቀበል ፈቃደኞች

101. እስመ ከማሁ አዘዘነ እግዚእነ እንዘ ሀሎነ ምስሌሁ በደብረ ዘይት ወይቤለነ ለእለኢይክሉ ተወክፎ ኢተሀብዎሙ ወኢታርእይዎሙ ከመኢይፅርፉ ስምየ ቅዱስ እስመአኮ ሐጥአን ዘየአቅቡ ቃልየ ወትእዛዝየ አላ ጻድቃን እለያፈቅሩ ቃልየ የአቅቡ ኵሎ።

## ምዕራፍ ፲፩ ነገር በእንተ ትስብእተ መድኅኒነ ወበእንተ ምፅአቱ ዳግም፣ ወካልአት ሥርዓታት

1. ንጽሕፍ ነገረ ዘነገሮ ጴጥሮስ ለቀሌሚንጦስ ተልሚድ ዘውእቱ ረድእ ብሂል ወአለበወ በእንተ ውሉደ ሰብእ ወበእንተ አፍቅሮተ መድኅኒተ ሰብእ።

2. በእንተ ፍቅረ ዚአነ በፈቃደ አቡሁ ሠረፀ ፍሬ ስብሐት ወበመዓዛሁ ምዕዘ ኵሉ ዓለም ወበደሐሪ መዋዕል ወረደ ኀበ ማርያም ድንግል ወገብረ ለርእሱ ባሥረ ግሩመ

2. ወለብሶ እምኔሃ ለድንግል ወላዲተ አምላክ ማርያም

ያልሆኑትንና አእምሮ ለሌላቸው ግን ቃሌ መዘባበቻ እንዳይሆን አይነግሩዋቸውም

101. በደብረዘይት ከሱጋር ሳለን ጌታችን ያዘዘን ይኸው ነው የእኔን ቃል ለመቀበልና እኔን ለመከተል ፈቃደኞች ላልሆኑ ምሥጢራቱን ገልፃችሁ አትንገሩዋቸው መንገዱንም አትግለጹላቸው የተቀደሰውን ስሜ እንዳይሰድቡ ቃሌን መጠበቅ ያለባቸው ሐጢአተኞች ሳይሆኑ ቅዱሳን ብቻ ናቸው ለዚሁ የተመረጡ

## ምዕራፍ ፲፩ ስለመድሐኔታችን ሰውመሆንና ስለዳግም ምፅአቱ ስለሌሎችም የቤተክርስቲያን ሥርዓቶች

1. ከዚህ ቀጥለን ቅዱስ ጴጥሮስ ለቀሌሚንጦስ ስለሰው ልጆች ስለመድሐኔታችን ኢየሱስ ክርስቶስ የገለፀለትን እንፅፋለን ቀሌሚንጦስ "ተልሚድ" ተብሏል ተልሚድ ማለት ተማሪ ማለት ነው።

2. ስለኛ ፍቅር ባባቱ ፈቃድ ምሥጋና ፍሬን በማብቀል ወደኛ መጣ በመልካም መዓዛነቱም ዓለምን አሳመረ። በኋለኛውም ዘመን ወደዓለም መጣና ከቅድስት ድንግል ማርያም ዘንድ አደራ ለራሱም መልካም ሥጋን አዘጋጀ።

2. የአምላክ እናት ከተባለችው ድንግልማርያምም ሥጋን ለበሰ

ወተወልደ በቤተልሔም ወይሁዳ ወተሰምዓ በኵሉ ምድረ ይሁዳ ወኤፍራት ወኑየ እም ሄሮድስ እስከ በፅሐ ግብፀ ዘውእቱ ቁስቋም ወአግአዘ ኵሉ እስክንድርያ ወምሥር ወቁዝ ወኵሉ አድያሚሃ ለግብፅ

3. ወካዕበ ገብአ በከመፅሐፍ በነቢይ ዘይቤ እምግብፅ ፀዋዕክዎ ለወልደየ ወገብአ ናዝሬተ ወሀገረገሊላ ወአምአዘ እስከ ባሕረ ጥብርያዶስ ወዓቢይ ባሕር እንተ ይእቲ ኢያሪኮ::

4. በከመ ይቤ ዘካርያስ ነቢይ ውእተ አሚረ ይወፅእ ማየሕይወት እም ኢየሩሳሌም ወመንፈቁ ይውኅዝ ውስተባሕር ቀዳሚት ወመንፈቁ ውስተ ባሕር ደሐሪት ውእተ አሚረ ይከውን ፩ እግዚአብሐር ወ፩ስሙ ወኵሉ ዘፀውዓ ስመ እግዚአብሔር ይድሕን::

5. ወበመዓዛሁ ምዕዙ ሐዋርያት ወአምዓዙ ኵሉ ዓለመ እምሥራቀ ፀሐይ እስከነዓረብ እምደቡብ እስከ ሰሜን ወኵሉ አፅናፈ ዓለም

6. በከመ ይቤ ሐዋርያ ንሕነሰኬ መዓዛሁ ለክርስቶስ ብነ ወበመዓዛሁ ቅዱስ ፈለሱ ገዳመ ወመነኑ ዓለመ ወበመዓዛሁ አጥብዑ ልበሙ ሰማዕት ወመጠው ነፍሶሙ ለሞት ሐዲጎሙ ዘመደ ወውሉደ ወመኒኖሙ ፍትወታተ ወጣዕመ

የይሁዳ ክፍል ከሆነችው የይሁዳ ምድር ቤተልሔምም ተወለደ የሱም መወለድ በመላዋ ምድረ ይሁዳና ኤፍራታ ዘንድም ተሰማች ከሄሮድስም ሸሽቶ ግብፅ ደረሰ በደብረቁስቋምም ተቀመጠ እስክንድርያን ምሥርና ቁዝን ጨምሮ አገሪቷን ነፃ አወጣ::

3. በነቢዩ ከግብፅ ልጄን ጠራሁት ተብሎ እንደተፃፈውም ከግብፅ ወደ ናዝሬት ተመለሰ ወደገሊላም ደረሰ የጥብርያዶስን ባሕር ጨምሮም እስከ ባህረኢያሪኮ ያሉትን አገሮች በመልካም መዓዛው አሳመራቸው::

4. ዘካርያስ ነቢዩ ስለዚህ ትንቢት ሲናገር በዛንጊዜ የሕይወት ውሃ ከኢየሩሳሌም ይፈሳል ግማሹ ወደመጀመርያዋ ባህር ግማሹ ወደኋለኛዋ ባሕር ይፈሳል በዛን ጊዜ አንድ እግዚአብሔር ይባላል ስሙም አንድ ይባላል:: የእግዚአብሔርን ስም በንፁህ ልቡና የሚጣራ ሁሉም ይድናል ብሏል

5. በሱ መዓዛነት ሐዋርያት መልካም መዓዛነታቸው ከምሥራቅ እስከምዕራብ ከሰሜን እስከደቡብ ያለውን ዓለሙን ሁሉ መልካም መዓዛ እንዲኖረው አደረጉ

6. ይህን አስመልክቶ ሐዋርያ እንዲህ ብሏል እኛ የክርስቶስ መዓዛ ያለን ነን በክርስቶስ ቅዱስ መዓዛም ቅዱሳን በምንና ወደገዳም ይገባሉ:: በክርስቶስ መዓዛም ሰማዕት ጥቡእን ሁነዋል ለሞትም ሥጋቸውን አሳልፈው ሠጥተዋል:: ዘመድንና ልጅንም ትተው

ገዘ ዓለም እስከ አጥብዐ።

7. ወበመዓዛሁ ለክርስቶስ መልአ ውእቱ አልባቢሆሙ ለመሐይምናን ኮኑ ወሰማያውያነ እንዘመሬታውያን እምመዓዛሁ ለክርስቶስ እም ነበአቡሁ እምሰማያት ተሠውጠ ውስተ ክርሣለማርያም ድንግል።

8. ወተሠውጠ መዓዛሁ እሙዳይ ውስተሙዳይ እስመይቤ አሐዱ እምነቢያት እፍረት ተሠውጠ እምከናፍረከ ኢይቤ ተክዕወ አላ ይቤ ተሠውጠ ስምከ እሙዳይ ውስተ ሙዳይ።

9. ወሙዳዩኒ ያምዕዝ ኩሎ ዓለመ ወለሊሁኒ ምዑዝ ወሙዳዩኒ ወተመዝሚዞ ሰብእ እየሐድግ መዓዛሁ ወከማሁ መዓዛሁ ለክርስቶስ ንሕነ ኵልነ መሐይምናን እለ ተጠመቅነ በአሚነ አብ ወወልድ ወመንፈስቅዱስ በቅድስት ቤተክርስቲያን።

10. ስማዕ ኦ ወልድየ ቀሌሚንጦስ ዘነገረኒ እግዚእየ ኢየሱስ ክርስቶስ ንጉሠ ሰማያት ወምድር ፈጣሬ ኩሉ ዓለም ከመ በደሐሪ የዐልው ብዙኃን ሃይማኖቶሙ ወይሴኩስ ፍቅር እምብዙኃን አሐው ወይመፅኡ ብዙኃን ሐሳውያን ነቢያት ወሐሳውያነ መሲሐን ወያስህቱ ሰብአ በእከየ ምግባሮሙ

ክርስቶስን ብቻ ተከትለዋል የዚህንም ዓለም ጣዕም ፈስመው ንቀዋል

7. በክርስቶስ መዓዛ የመሃይምናን ልቡና ይሞላል መሬታውያን እያሉም ሰማያውያን ሆኑ በምድር ሁነው እያለ ከሰማያውያን ጋር እንዳሉ ሁነው ታዩ የክርስቶስ መዓዛነት ካባቱ ከሰማያት ከመሆኑ የተነሳ በቅድስት ድንግል ማርያም ከርስ አደረ ካባቱ ዘንድም ወደዓለም ተላከ

8. የክርስቶስ መዓዛነት ከሙዳይ ወደሙዳይ ተጨመረ ከነቢያት አንዱ ከሙዳይ ወደሙዳይ ዕፍረት ከከንፈርህ ይጨምራል ብሏል ነቢዩ ፈሰሰ አላለም ስምህ ከሙዳይ ወደሙዳይ ተጨመረ አለ እንጂ።

9. ይህም የመዓዛ ሙዳይ ዓለምን ሁሉ መልካም መዓዛ አድርጎታል ሙዳዩም የመልካም መዓዛ ሙዳይ ነው በመልካም መዓዛ የሰው አስምሮ መልካም መዓዛነቱን አይለቅም የክርስቶስ መዓዛም እንዲሁ ነው። እኛ መሐይምናን ሁላችን በሥላሴ የተጠመቅን ምእመናን ሁሉ የሱ መዓዛነት አለን

10. ልጄ ቀሌሚንጦስ ሆይ ስማኝ ጌታችን ኢየሱስክርስቶስ የሰማያትና የምድር ጌታ ዓለምን ሁሉ የፈጠረ በኋለኛው ዘመን ብዙዎች ሃይማኖታቸውን እንደሚክዱ ፍቅርም በወንድማማች መካከል እንደምትጎድል ብዙ የሐሰት ነቢያትም እንደሚመጡና ሰውን ከቀናች ሃይማኖቱ በመጥፎ ተግባራቸው እያሳሳቱ

ወበሃይማኖቶሙ ርኩስት፡፡

11. እስመለቀረቦቱ ለሕልቀተዓለም ያመፅኡ እኩየ ምግባረ እንተ ኢኮነ እምቅድስት ቤተክደርስቲያን ውእተ አሚረ ሠይጣን ይረክብ ምክንያተ ኀቤሆሙ ከመ ያስሕት ሰብአ እስመ ይረክብ ፍኖተ በውስተ ቃሎሙ ወእለ ስሕቱ ይበክዩ፡፡

12. አኮ ለሊሆሙ ባሕቲቶሙ ዘስሕቱ ወኃጉሉ አላ ባእዳነሂ ያስሕቱ በትምይንቶሙ በውእቶን መዋዕል ይከውኑ ኖሎት ገፋዕያነ መርዔቶሙ ወኢይትዌከፉ ንስሐሆሙ፡፡

13. አሌሎሙ ለእለ ከመዝ በእለተ ኰነኔ አመይቀውሙ ቅድመ ምኵናኑ ለእግዚአብሄር እስመ ያቀድም ገሥፆ ኪያሆሙ ወእም ድሕሬሆሙ ለአሕዛብ እለኢአቀቡ ቃሎ ወትእዛዞ ለእግዚአብሔር ይስሕብዎሙ ውስተኰነኔ

14. በውእቱ ወዋዕል ይመፅእ ንጉሥ እኩየምግባር ገበሪሃ ለእከይ ወይሠርቅ ፀሐይ እንተ ምዕራብ ወወርህኒ እንተ ኤላም ይእተ አሚረ ትትነሣእ ዛብሎን ወንፍታሌም ክሳዳ ታነውሕ ወቅፍርናሆም ትትሜካህ ወይትሐሰያ ኮራዚ

እንዲርቅ እንደሚያደርጉ ይህንንም የሚደርጉት በረከሰው እምነታቸው እንደሆነ ነገረኝ

11. የዓለም መጨረሻ ሲቃረብ እነሱ መጥፎ ሥራን ያመጣሉ ይህም ከቅድስት ቤተክርስቲያን ሥርዓት ውጭ ነው በዚህ ጊዜ ሠይጣን መግቢያ ያገኝና ሰዎችን የማሳሳት ተግባሩን ይቀጥልበታል እነሱንም መሣርያ እያደረገ ሰዎች እንዲሳሳቱ ያደርጋል በቃላቸውም መንገድ እያገኘ ይሄዳል የተሳሳቱም ያለቅሳሉ

12. የሚስቱት ብቻቸው አይደሉም ሌሎችንም ያሳስታሉ ተንኮለኞች ናቸውና በዚህ ጊዜ የእግዚአብሔርን መንጋዎች እንዲጠብቁ የተመደቡት እረኞች ካህናት መንጋዎቻቸውን የሚበትኑና ከንሥሐልጆቻቸው ንሥሐን የማይቀበሉ ይሆናሉ

13. ይህን በመሰለ አካሄድ ሕይወታቸውን ለሚመሩ ካህናት እግዚአብሔር ለፍርድ በሚመጣበት ጊዜ ከፊቱ በሚቆሙበት ጊዜ ወዮላቸው ከሁሉ አስቀድሞ እግዚአብሔር ከገሠፃቸው በኋላ ወደዘለዓለም እሳት ያሰናብታቸዋል ከነሱ በኋላ ደግሞ ትእዛዙን ያልጠበቁትን ሁሉ ይገሥፃቸዋል ካህናቱን ተከትለው ገሐነመእሳት እንዲወርዱ ያደርጋል

14. በዚህ ወቅት ሥራው ክፋት ብቻ የሆነ ንጉሥ ይመጣል ከምዕራብ በኩል ፀሐይን ያወጣል ጨረቃን ደግሞ ከድርጊት ማውረጃ ያወጣል (ኤላም የድርጋት ማውረጃ ብሎታል መዝገበቃላቱ) በዚህ ጊዜዛብሎንና ንፍታሌም አንገታቸውን

ወቤተሳይዳ እስመ ይመስላሁ ለውእቱ ብእሲ ከመክርስቶስ ወሶበርእየ ምግበሮን ይትሐፈር።

15. እስመ ኢኮነ ርቱዓ ዘይርኢ አላ ኵሉ ግብሩ በአድልዎ ይእተ አሚረ ይከልእ እግዚአብሔር ዝናመ እምሰማይ ወይከውን የብሰ ክረምት ወትተርፍ ምድር ዘእንበለ ጠል ወአውል ወይከውን ዝናመ ምድር ቆባረ ወአውሎ።

16. ወአንቅዕተ ማያት ኢይሁቡ ነቅዐ ማየ ባሕር ይከውን የብሰ ወየሐዕራ እማንቱ መዋዕል እኩያት በከመ ተነግረ በወንጌል ወሶበ ኢሐፀራ እማንቱ መዋዕል እምኢድኅነ ኩሉ ዘነፍስ ባሕቱ በእንተ ሕሩያኒሁ የሐፀራ እማንቱ መዋዕል።

17. ቀዲመሰ ይቀውም ውስተ ኢየሩሳሌም ሀገሩ ለንጉሥ ዓቢይ ወእምዝ ውስተኵሉ ዘተሰምየ ምሥዋዓ ወይቤ ሥግዱ ለአምሳለ ዚአየ።

18. ወባእደሰ ተእዛዘ ለልየ ዘአዘዝኩ ቀዳሚ ኢትግበሩ ብዙኀን እለይብሉ በይእቲ ዕለት እፎ ኢነገረነ እግዚእነ ከመ ይሥእሮሙ ለወንጌል ወለጳውሎስ ወለግብር ወለኵሎሙ መጻሕፍቲሆሙ ወኢነገረነ ክርስቶስ ከመ ይነሥቶሙ

ያስረዝማሉ ቅፍርናሆም ትመካለች ኮራዚና ቤተሳይዳ ይደሰታሉ ይህን በእከይ የተነሳው ንጉሥንም ክርስቶስ ነው ይሉታል በኋላ ግን ይህንን የጥፋት አካሄዳቸው ሲመለከቱ እጅግ ያፍራሉ።

15. ይህ የሐሰት ንጉሥ አመራሩ የተበላሸና በአድላዊነት የተበከለ ነው። በዚህ ጊዜ የሰው ሐጢአት ከመብዛቱ የተነሳ ተፈጥሮ ታምፃለች እግዚአብሔር ዝናምን ይከለክላል ክረምት ያደርቃል ምድር ያለጠልና ያለልምላሜ ትቀራለች በዝናም ምትክ በምድር ላይ አቧራና ትብያ ዓየሩን ይሸፍኑታል።

16. የውሃ ምንጮች ውሃን አያመነጩም ባሕር ይደርቃል እነዚህ ክፉ ቀኖች ግን ያጥራሉ እነሱ ባያጭሩ ነፍስ ያለው ፍጡር ሁሉ ባልዳነም ነበር ነገር ግን በእግዚአብሔር ስለተመረጡና በእግዚአብሔር ፈቃድ ሕይወታቸውን ስለመሩና ቅድስናቸውን ስላላረከሱ ቅዱሳን እነዚህ ዘመኖች ያጥራሉ

17. ይህ መሥሐቲ ንጉሥ አስቀድሞ የታላቁ ንጉሥ አገር በሆነችው ኢየሩሳሌም ላይ ምስሉን በማስቀመጥ ስገዱልኝ ይላል ቀጥሎ መሥዋእት በተፈፀመባቸው ሁሉ እንዲሠገድለት ሕዝቡን ያዛቸዋል

18. ከዚህ በፊት ያስቀመጥኩትን ትእዛዝ አንስቻለሁና ሠርዙት ይላል ሐሳዊመሲህ ነውና በዚህ ጊዜ የክርስቶስ ወንጌልና ጳውሎስ፣ ግብረሐዋርያትንና የሕግ መጻሕፍትን እንደሻራቸው አልነገረንም በማለት የሱን ሐሳዊመሲሕነት ይረዱታል መጻፎቹን

ለመጻሕፍቲሁ።

19. ንሕነሰ ኢንሰምዖ ለዝንቱ ነገር ወበ እለይጕይዩ ወየሐድጉ አዝማዲሆሙ ወሰብአቤቶሙ ወይትሐብኡ በበአታት በከመይቤ ኢሳይያስ ነቢይ ሁር ሕዝብየ ወባእ ቤተከ ---- ወእለሰ ኢይፈርሑ ትግርምቶ የሐውሩ ኀቤሁ ወይፀርፉ ላዕሌሁ ወይ ትመተር አርእስቲሆሙ ወይከውኑ ሰማዕተ ወይበፅሕ ዘተብህለ በወንጌል።

20. እምከመ ለምለመ አዕፁቂሁ ለበለስ አእምሩ ከመ በፅሐ ጊዜሁ ለማእረር ብሂል ሠረፀ ፀለስኬ ይስመዩ እማዕተ።

21. ወእምድሕሬሁ ይወርዱ ሄኖክ ወኤልያስ ይስብኩ ወያስተሐፍርዎ ለውእቱ መምዕላይ ፀሩ ለጽድቅ ወልደለሐሰት ሶቤሃ ይትመተር አርእስቲሆሙ።

22. ወያነሥእዎሙ ሚካኤል ወገብርኤል ወይወስድዎሙ ውስተ ገነተ ትፍሥሕት ወንጥበተ ደሞሙኒ ኢትወድቅ ዲበምድር።

23. ወለደሐሪኒ ፀላኢ ይስዕሮ ሞት ወይመፅእ እግዚአብሔር እምሰማይ ከመያቅም ኪዳነ መንግሥቱ ምስለ ሕሩያኒሁ ወይትነፋሕ ቀርን ፫ጊዜያተ በአፈ ሚካኤል ሊቀመላእክት

እንደሚያመስሳቸው ክርስቶስ አልነገረንም እስከማለት ይደርሳሉ።

19. ይህንን የስሕተት ቃል አንሰማውም ይላሉ ከዚሁ ክህደት ለመራቅ ሌሎች ቤተሰቦቻቸውንና ዘመዶቻቸውን ትተው ወደየዋሻውና ወደየተራራው በመግባት ይደበቃሉ ለዚሁም መሠረት የሚያደርጉት ነቢዩ ኢሳይያስ ሕዝቤ ሆይ ሂድ ቤትህም ግባ የእግዚአብሔር መዓት እስኪያልፍ ድረስም ለጥቂት ጊዜ ተደበቅ ያለውን ነው ሌሎች ደግሞ ፊትለፊት ተጋፍጠው አንገታቸውን ለሠይፍ ይሠጣሉ ሰማዕትነትንም ይቀበላሉ በዚሁ በወንጌል የተጻፈው ይፈፀማል።

20. ከወንጌል የተጻፈው የበለስ ቅርንጫፍ ከለመለመ በዛን ጊዜ ጊዜው እንደደረሰ እወቁ የሚለው ሲሆን የበለስ ቅጠል ብሎ የገለፃቸው እነዚያ የተሰደዱትና ሰማዕትነትን የተቀበሉ ደጋግ ናቸው።

21. ይህ ከሆነ በኋላ ሄኖክና ኤልያስ ከገነት ወርደው ይሰብካሉ ያንንም ከሐዲ የፅድቅ ጠላት የሐሰት ልጅ ያሳፍሩታል በዚሁም በሠይፍ ይቆረጣሉ

22. ሚካኤልና ገብርኤልም አንስተው ደስታ ወደተሞላበት ገነት ያስገቡዋቸዋል ከደማቸው ጠብታ አንዷ እንኳ አትነጥብም

23. ኋለኛውን ጠላት ግን ወድያው ከመነሳቱ ሞት ይሽረዋል በዚህ ጊዜ እግዚአብሔር ከመረጣቸው ቅዱሳኖቹ ጋር ቃል ኪዳን የገባላትን ቃሉ ለመፈፀም ይመጣል መለከትም በመላእክት አለቃ

በቀዳሚ ንፍሐተ ቀርን ይትጋብኡ ሥጋት እለኩ ከመፀበል ወበዳግም ንፍሐተ ቀርን ይትረሐው አብያት ዘውስቴቶሙ ተዘግቡ ነፍሳት ወይገብኡ ውስተ ሥጋት በጠለ ሞሕረት እንተ ትወርድ ኀቤሆሙ እምኀበ እግዚአብሔር።

24. በከመይቤ ኢሳይያስ እስመጠል ዘእምኀቤከ ሕይወቶሙ ውእቱ ወበሣልስ ንፍሐተ ቀርን ይትነሥኡ ምውታን ከመቅዕበተ ዐይን ወያቀውሞሙ ቅድመ ገፁ አመ ያቀውም አባግዓ በየማኑ ወአጣሌ በፀጋሙ ወይቤሎሙ ርጉማን ለእለ ኢአቀቡ ትእዛዞ ወይሠስድዎሙ ውስተ ብካይ ወሐቅየ ስነን ወጽልመት።

25. ጻድቃንሰ እለ በየማኑ የሐውሩ ውስተ ሕይወት ዘለዓለም ኀበ አልቦ ደዌ ወሕማም ኀበ ኢይመውቱ እምዝ ዳግመ ኀበ ገነተ ተድላ ወትፍሥሕት ወፍሥሐሆሙ ኢየኀልቅ ለዘለፋ እስከ ለዓለመ ዓለም።

26. ወለኃጥአንሰ ኢየሐልቅ ኩነኔሆሙ ለዝሉፋ እስከ ለዓለመ ዓለም ወነፍሳቲሆሙ ኢይመውታ እስከ ለዓለመ ዓለም።

27. ዝንቱ አመ ይከውን ዕለት ግርምት ወዕለተ ብካይ ወፍርሐት ወረአድ አሜሃ ጻድቃን ይበክዩ በእንተ ሐጥአን

ሚካኤል አፍ ይነፋል የሚነፋውም ሦስት ጊዜ ነው በመጀመርያው የመለከት መነፋት ወደትቢያነት የተለወጠው ሥጋ ሁሉ ይሰበሰባል በሁለተኛው የመለከት መነፋት ነፍሳት የሠፈሩባቸው አብያተመዛግብት ይከፈታሉ ነፍሳትም ከመዛግብቱ ይወጣሉ ከመዛግብቱ ወጥተውም ወደየራሳቸው ሥጋ ይገባሉ ከእግዚአብሔር ዘንድም ወደነሱ ጠለምሕረት ትወርዳለች።

24. ይህን ሲያመለክት ኢሳይያስ የጠል መነሻው ካንተ ዘንድ ነው ብሏል በሦስተኛው የመለከት መነፋት ሙታን እንደዓይን ቅፅበት ፈጥነው ይነሳሉ በጎችን በቀኝ ፍየሎችን በግራ እንደሚያቆምም ከፊቱ ያቆማቸዋል በግራ ለቆሙትና ትእዛዙን ላልጠበቁት ርጉሞች በማለት ዘልፎ ያሰናብታቸዋል ወደመከራና ወደጨለማ ቦታ ለመወሰድም እያለቀሱ አጋንንት ይረከቡዋቸዋል

25. ጻድቃን ግን በቀኝ ቆመው ፈጣሪያቸውን ካመሰገኑ በኋላ ወደዘለዓለማዊው ህይወት ይገባሉ ከዚሁ ደዌና ሕመም የለም ዳግመኛም በዚያ ሞት የለም ቦታው የተድላና ደስታ ቦታ ነው ደስታቸው አያልቅም ዘወትር እስከዘለዓለም ይኖራል እንጂ

26. የሐጥአን ሥቃያቸውና መከራቸውም እስከለዓለም አያልቅም ዘወትር ያለመቋረጥ እያለቀሱና እየተሠቃዩ ይኖራሉ እንጂ ነፍሳቸውም ከስጋ አትለይም

27. ይህ ሁሉ የሚፈፀምባት ዕለት አሥፈሪ ዕለት ናት የልቅሶና የፍርሐት ዕለትም ናት ጻድቃን ስለሐጥአን የሚያለቅሱበት ዕለት

ወሐጥአን ይበክዩ በእንተ ኃጢአቶሙ መላእክተ ሰማይኒ ይበክዩ በእንተ ሐጥአን ወበይእቲ ዕለት ይገብዕ ኩሉ ውስተ ርስቱ እለሠናየ ገብሩ ውስተ ማሕደረ ሕይወት ወእለሰ እኩየ ገብሩ ውስተኵነኔ ዘለዓለም።

28. ዘንተ ሐልዩ ወአርትዑ ልበክሙ ለእግዚአብሔር በከመ ነገርናክሙ ቀዲሙ በእንተ ሥርዓተ ቤተክርስቲያን ቅድስት በከመ መሐረነ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ኢታስተሐፍርዎሙ ለእለ ፩ እምንኡሳን እለ የአምኑብየ።

29. ወይቤለነ መላእክትየ ዘልፈ ይሬእዩ ገፀ ለአቡየ ዘበሰማያት እሉኬ ካህናት ንኡሳን እለ ቤተክርስቲያን እለቦሙ ልቡና ወአእምሮ ሰብ ይነግሩዎሙ ለነገሥት ወለመኳንንት ያስተሐቅርዎሙ ወኢሰምዑ ቃሎሙ ዘነገሩዎሙ።

30. ወአነሂ እኴንኖሙ በከመ እከየ ምግባሮሙ እንዘ እሙንቱ ይከውንዎሙ ስሞዓ በኀቤየ ኢታስትቱ ነገሮሙ እምዘአዘዝኩክሙ አልብክሙ ኃጢአት።

ናት ሐጢአተኞች ደግሞ ስለሐጢአታቸው የሚያለቅሱበት እለት ናት የሰማይ መላእክትም ስለሐጢአተኞች የሚያለቅሱባት ዕለት ናት በዚች ዕለት ሁሉ ወደየርስቱ ይገባል መልካም የሠሩ ወደሕይወት ማደርያ የሚገቡበት ዕለት ናት ክፉ የሰሩም ወደዘላዓለምኩነኔ የሚገቡበት ዕለት ናት

28. ወንድሞቼ ሆይ ከዚህ በላይ የተገለጸውን አስቡ አስተውሉ ችላ አትበሉት ልቡናችሁም ለእግዚአብሔር ክፍት አድርጉት ይህንንም ስለስርዓተቤተክርስቲያን ስናስተምራችሁ ገልጸንላቹኋል ይህንንም ጌታችን ኢየሱስክርስቶስ ነው ያስተማረን ጌታችን እኔን ከሚያምኑ ሁሉ አንዱን ትንሽ ነው ብላችሁ አታቃልሉት ብሉናል።

29. ጌታችን ኢየሱስክርስቶስ መላእክቶቼ በሰማይ ያለውን አባቴ ዘወትር ያዩታል ብሎናል መላእክት የተባሉት ካህናት ናቸው ልቡናና አእምሮ ያላቸው ካህናት እውነተኞች ካህናት ናቸው እነዚህ ካህናት መኳንንትና ነገሥት ስላስተማሩዋቸው ይንቋቸዋል ያቃልሉዋቸዋል።

30. ካህናትን ያቃለሉ ሁሉ እኔ ወደኩነኔ አስገባቸዋለሁ። ካህናቱም ለጥፋታቸው ምስክሮች ይሆኑባቸዋል የካህናት ንግግር አታቃልሉ ነገራቸውን ተቀበሉ እንጂ ካህናት ያዘዙዋችሁን ሁሉ በትክክል ፈፅማችሁ የቅድስት ቤተክርስቲያን ልጅነታችሁን ከጠበቃችሁ ሐጢአት የለባችሁም።

31. እስመ በእንቲአክሙ ይተግሁ ኵሎ ዕለተ መዓልተ ወሌሊተ ወይሥእሉ ሥርየተኃጢአትክሙ ዲያቆናትኒ ተባደሩ በእንተ መልእክትክሙ ከመ እስጢፋኖስ ሰማዕት ውእቱ ምውቅ በመንፈስ ቅዱስ ወሶበ ይወግርዎ ርዕየ ሐዋህወ ሰማይ ርሕወ ወወልደ እግዚአብሔር ይነብር በየማነ አብ ወተፈሥሐ በዝየ።

32. ወከማሁ ኮኑ ዲያቆናት በአርአያ እስጢፋኖስ ሰማዕተ ክርስቶስ ወአዲ ርእየ እስጢፋኖስ መንፈስ ቅዱስ እንዘ ይወርድ ዲበ ምሥዋዕ በውስተውሳጤ መንጦላዕት ወሶበ ርእየ ተፋየፀ ከማሁ ዲያቆናትኒ ይትፋፀዩ በርደተ መንፋስ ቅዱስ።

33. ሶበይብል ካህን ፈኑ ፀጋ መንፈስ ቅዱስ ዲበ ዝንቱ ኅብስት ወፅዋዕ ዘቤተ ክርስቲያን ደቂቀ መንፈስቅዱስ ዲያቆናት እለ አንፅሑ ርእሶሙ ይሬእዩ እንዘ ይወርድ መንፈስቅዱስ ላዕለመሥዋዕት ዘቤተክርስቲያን ወአዲ ይረክቡ መንበረ ልዑለ ከመ እስጢፋኖስ ቀዳሜ ሰማዕት በመንግሥተ ሰማያት።

34. ወእለሰ ኢያሰነዩ መልእክቶሙ ይበውኡ ውስተጸናፌጽልመት ምስለ ዲያብሎስ ወምስሌሁ ይነብሩ

31. ካህናት ሁልጊዜ ሌት ተቀን ስለናንተ የኃጢአት ሥርየት ተግተው ይፀልያሉ እግዚአብሔርንም ከመለመን አያርፉም እናንተም ዲያቆናት እንደ እስጢፋኖስ ሁኑ እስጢፋኖስ በመንፈስቅዱስ ልቡ የሞቀ ነው በድንጋይ ሲደበድብ ሰማይ ተከፍቶ ወልድ በአብ ቀኝ ተቀምጦ በማየቱ በደስታ ተሞላ።

32. ዲያቆናት እንደእስጢፋኖስ ይሁኑ እስጢፋኖስ የክርስቶስ የመጀመሪያው ሰማዕት ሁኗልና ዳግመኛም እስጢፋኖስ በመጋረጃ ውስጥ ወዳለው መሥዋዕት ቦታ መንፈስቅዱስ ሲወርድ አይቶ አንፋጨ ዲያቆናትም ልበንፁሆች ሁነው የመንፈስቅዱስ ርደትን በማየት ለማንፋጨት እንዲበቁ ተግተው በትህትና ተልእኮአቸውን ያከናውኑ።

33. ካህን የመንፈስቅዱስን ፀጋ ላክ ባለጊዜ በቤተክርስቲያን ውስጥ ለመስዋዕትነት በቀረቡ ፅዋዕና ሕብስት ላይ መንፈስቅዱስ ይወርዳል (ገፅ ፺፮ በብራናው) ዲያቆናት በቅድስና ሥጋወደሙን ለመለወጥ ሲወርድ ለማየት ይችላሉ። የዲያቆናት ክብር በዚህ ብቻ የተወሰነ አይደለም ቅዱስ እስጢፋኖስ በመንግሥተሰማያት ታላቅ የክብር ቦታ ከእግዚአብሔር ዘንድ ሊሠጠው እንደቻለ ለነሱም ይሠጣል።

34. በዲቁና እንዲያገለግሉ የተሠጣቸውን ተልእኮ በንፅሕናና በቅድስና ሁነው ካላገለገሉ ግን ዕድል ፋንታቸው ዲያብሎስ ከተከታዮቹ

ለዝሉፉ።

35. አዝዝ አ ወልድየ ቀሌሚንጦስ ከመ ይገሥፁዎሙ ለእለይሬእዩ መርዔቶ ለክርስቶስ ከመ ይገሥፁዎሙ ለሕዝብ ይፍርሑዎሙ በአላንቱ ቃላት ዘይገብር ግልፎ በቤቱ ርጉም ውእቱ በኦፍ ዘይጤየር ከማሁ ርጉም ውእቱ።

36. ዘያስተአኪ አባሁ ወእሞ ወያነጥዮሙ በኵሉ ወያስተሐምሞሙ እስከ ይግዕሩ ኀቤየ ይትኄነኑ በኀበ እ፝ዚአብሔር።

37. ዘያስሕቶ ፍኖተ ለዕውር ወይነግሮ ሕሱመ ለፅሙም ውጉዝ ወርጉም ውእቱ ዘያስተአኪ ኵሎ ሥርዓተ ዘተነግረ በቀኖና ዘቅድስት ቤተክርስቲያን ውጉዝ ውእቱ

38. ዘኢያፈቅሮ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወዘኢየአምን በአብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ ወበቅድስት ቤተ ክርስቲያን ርጉም ወውጉዝ ውእቱ።

39. ዘኢየአምን ከመ እግዚአብሔር ገብረ ሰማያተ ወምድረ ባህረ ወየብሰ ወኵሎ ዘውስቴቶሙ ዘኢየአምኖ ለአብ ከመአብ

አጋንንት ጋር ወዳለበት የጨለማ ቦታ ይገባሉ እስከዘለዓለምም በዚያ ይኖራሉና

35. ልጄ ቀሌሚንጦስ ሆይ የቤተክርስቲያን ካህናት የሆኑ ሁሉ በመጨረሻው ዘመን ሰው ሁሉ እንደሚቀርብና ይህንንም ህዝቦቹ ፈርተው ከክፉ እንዲጠበቁ ይመክሩዋቸው ዘንድ እዘዛቸው በቤቱ ጣዖት አስቀምጦ የሚያመልከው ካለ የተረገመ ነው እንዲሁም በወፍ የሚያሟርትና ሌላም ተመሳሳይ ጣዖት መንገድን የሚከተል ሁሉ የተረገመና የተወገዘ ነው።

36. አባትንና እናቱን አክብሮ የማይታዘዝና በፈለጉት ሁሉ ትእዛዛቸውን የማይፈፅም ልጅ የተረገመ ነው ወላጆች በልጆቻቸው ክፋት ወደእግዚአብሔር ይጮኻሉ እግዚአብሔርም ያዝንላቸዋል።

37. ዐይነሥውሩን ትክክለኛውን መንገድ ከማሳየትና ከመምራት ይልቅ ወዳልሆነ አቅጣጫ የሚመራ የተረገመና የተወገዘ ነው። መስማት የተሳነውንም አይሰማኝም ብሎ ያልሆነ ንግግርንና ስድብን የሚናገርም ርጉም ነው።

38. ጌታችን ኢየሱስክርስቶስን የማይወድ፣ በአብ በወልድና በመንፈስቅዱስ እንዲሁም በቅድስት ቤተክርስቲያን የማያምን የማይቀበል የተረገመና የተወገዘ ነው።

39. ሰማይንና ምድርን ባሕርንና የብስን በውስጣቸው ያለውም ሁሉ የፈጠረ እግዚአብሔር መሆኑን የማያምን እንዲሁም አብ

ውእቱ ወለወልድ ከመወልድ እምቅድመዓለም ርጉም ውእቱ።

40. ወመንፈስቅዱስሂ ሥሉስ ውእቱ እምአብ ዘይወፅእ ወእምወልድ ዘይነሥእ ወሰለስቲሆሙ በአሐቲ ምክር ገብሩ ሰማያተ ወምድረ።

41. ሰማዕ ዘይቤ በቃለ እግዙአብሔር ፀንዓ ሰማያት ወእምእስትንፋሰ አፉሁ ኩሉ ኃይሎሙ ርጉም ውእቱ ዘኢየአምን ከመሕልው በመለኮቱ ወምሉእ ሰማያተ ወምድረ።

42. ወእመሰቦ ዘይብል ኢሕልው እግዚአብሐር ውስተኵሉ መካን ኢያእሚሮ ወኢለቢዎ ዘይብል ውእቱ ኢይረኩስ ወኢያረኩስ አላ ኵሎ ይቄድስ ርጉም ውእቱ።

43. አገዙዎሙ ኢይፈፅሙ ደቃቃተ ኃጣውአ በነፅሮ አዓይንት ወበሰሚዓ ዕዝን ወበገሲሰ እድ ወበሠሪቀ ወበሐስዎ በቃል ወበልሳን በከመይቤ ዳዊት ኢይንብባ አፉየ ግብረ እጓለ እመሕያው። እሉ እሙንቱ ደቂቃት እለያረኩሱ ዘገብሮሙ።

44. ርኩስ ወስዑብ ውእቱ ዘየሐውር ውስተዘፈን ወተውኔት እንዘክርስቲያናዊ ውእቱ ይቁም እምቤተክርስቲያን እስከይፌፅም ንሥሐሁ።

45. እግዚአብሔር ይቤ አነ እግዚእሙ ለነሳሕያን ዘእትዌከፎ

አባትመሆኑን ወልድም ከዓለም በፊት ጀምሮ ልጅ መሆኑን የማያምን የተረገመ ነው።

40. ሦስተኛው አካል መንፈስ ቅዱስ ከአብ እንደወጣ ሦስቱ አካላት ባንዲት ምክር ሰማይንና ምድርን እንደፈጠሩ የማያምን የተረገመ ነው።

41. በእግዚአብሔር ቃል ሰማዮች ፀኑ በአፉ እስትንፋስም ኃይላቸው ሁሉ ቆመ ያለውን ስማ። እግዚአብሔር በመለኮቱ ሰማያትንና ምድርን የሞላ መሆኑንና ዘለዓለማዊ መሆኑን የማያምን የተረገመ ነው።

42. እግዚአብሔር ባልተባረከ ቦታ አይገኝም የሚል ካለ እግዚአብሔር ሁሉን የሚቀድስ እንጂ የሚረክስ ወይም የሚያረክስ አይደለም የሚለውን አላስተዋለምና የተረገመ ነው።

43. ክርስቲያኖች ስሕተት መስለው የማይታዩትንም እንዳይፈፅሙ እዘዙዋቸው እነሱም በዓይን በማየት በጆሮ በመስማትና በእጅ በመዳሰስ የሚፈፀሙ ናቸው በንግግር የሚፈፀም ሐጢአትም ከነዚሁ ይቈጠራል እነዚህ ወደሐሰትና ወደሥርቆት ስለሚወስዱ በፈፀማቸው ላይ ርኩሰትን ያመጣሉ።

44. ክርስቲያን ሁኖ ወደዘፈንና ወደ ጭፈራ ቤት ከገባ ለተወሰነ ጊዜ ወደቤተክርስቲያን እንዳይገባ ይከላከላል ከካህናት ንሥሐውን ከተቀበለ በኋላ ግን ወደቤተክርስቲያን ይግባ።

45. እግዚአብሔር በፍፁም ሕሊናቸው ለሚመለሱ ነሳሕያን

ለሐጥእ እምከመነስሐ ርኩስ ወስዑብ ውእቱ ዘያደሉ ፍትሐ ለእጓለማውታ ወኢያነግፎ ለግፉዕ እምእደ ዘይትሄየሎ ኃጥአንሰ ወመፀብሐን ያፈቅሩ መሢጠ።

46. እመቦ ዘቀሠጠ እምቤተክርስቲያን ተብሕለ በቀኖና ይወስክ ዲቤሁ ፰እደ ወእምድሕሬሁ ይነስሕ ወይባእ ወይትከነስ ወይቅረብ ርኩስ ውእቱ ዘያመጉዕ ሊቃናተ እለይትኤዘዙ አግብርተ ለእጋእዝተ፡ሆሙ።

47. ርኩስ ውእቱ ዘይሁብ ሕልያነ በእንተ ሢመተክህነት እንዘኢይደልዎ ይሰየም። ርኩስ ውእቱ ዘይዘብጥ ቀሲሰ ወዲያቆነ ወኩሉ ዘይፈቱ ዐመፃ ርኩስ ውእቱ።

48. ቤተክርስቲያን ይእቲ እንተ መላእክት ወማሕበረ ቅዱሳን ሕቡረ ይሴብሁ እግዚአብሔርሃ ወይትፌስሑ በውስቴታ በመርዓዊሃ ሰማያዊ ወንሕነኒ ንዕቀብ ፍናዊሃ በኩሉ ጊዜ እስመ መርዓት ዘንጉሥ ነፍሰ ክርስቲያን ወበነቢያት ይትነገር በበመትልው እምንበእዝራ ስባሔ፣ ወእምንበ ዳዊት ከበሮ ወመሰንቆ።

49. ንሕነኒ ውስተ ሐይላ ንደይ ልበነ ንዴግና ወንበላ በሐ ወትረ ንሳለማ ለቅድስት ቤተክርስቲያን በከመ አዘዘነ

ጌታቸው እኔ ነኝ አለ። ሐጢአተኛው ንስሐ ከገባ እቀበለዋለሁ አለ። ለሙት ልጆችና ለድሆች ፍርድን የሚያጓድል እጅግ የረከሰ ነው ሰው ጥቃት እየደረሰው እያየ የማይገለግለው የተወገዘ ነው ኀጢአተኞችና አስገባሪዎችስ ነጣቂዎች ናቸው።

46. ከቤተክርስቲያን ንብረት የሰረቀ ሰው ቢገኝ ከሠረቀው በአምስት እጅ አብልጦ ይከፈል ከዚያ በኋላ ንስሐ ይግባና ወደቤተክርስቲያን ተመልሶ ከማሕበር አንድነት ይኑረው። ሊቃውንትን የሚያቃልል ርኩስ ነው እነሱ በአገልግሎት ለቤተእግዚአብሐር የሚታዘዙ ናቸውና።

47. የካህናትን ሥልጣን ለማግኘት መማለጃ የሚሠጥ የረከሰ ነው ይህንንም በማድረጉ ከቤተክርስቲያን ይባረር በንሥሐም ይመለስ ቄስንና ዲያቆንን የሚደበድብና ሌላም በደል የሚፈፅም የረከሰ ነው።

48. ቤተክርስቲያን መላእክት ከቅዱሳን ማሕበር ጋር ባንድነት እግዙአብሔርን የሚያመሰግኑባት ናት በሰማያዊው ሙሽራም ደስ ይሰኙበታል እኛም በሮቿንና መንገዶቿን በጥንቃቄ እንጠብቅ የሰማያዊው ንጉሥ ሙሽራ የክርስቲያን ነፍስ ትባላለች። ይህም በመከታተል ነቢያት ተናግረውታል ከዕዝራ ምሥጋና ከዳዊት ከበሮና መሰንቆ ለቤተክርስቲያን ተዘጋጅተዋል።

49. እኛም በቤተክርስቲያን ኃይል ልቡናችንን እንጨምር እንከተላት ሰላምም እንበላት ስለዚህም ጌታችን መድሐኒታችን ኢየሱስ

እግዚእነ ፍኖተ አሕዛብ ኢትሁሩ ወሀገረሳምር ኢትባኡ ሀገረሳምርሰ ኀበተዔወው ደቂቀ ኗኤል በናቡከደነፆር ምስለ ንጉሦሙ ወካህናቲሆም ኤርምያስ ከመይትነበይ ሎሙ በህየ ወኢያርስአሙ ቃለ እግዚአብሔር በውስተ ዔዋሆሙ።

50. ሶበ ተመይጦሙ እግዚአብሔር ከመይግብኡ ውስተብሔሮሙ ይቤልዎ አቤሜሌክ ወባሮክ ለኤርምስ ነዓ እስመ እግዚአብሔር ላዕሌነ ወይሰይም ለነ ካህናተ ከመቀዲሙ ወመማክርተ ወ፦ኳንንተ ከመ ትካት ባሕቱ ኢታምፅእ ምስሌከ ሰብአ ከሐድያን።

51. ኢተሀቡ ውሉደክሙ ለውሉዶሙ ወኢትንሣእ ወለቶ ለወልድከ ባሕቱ ንዑ እስራኤል ባሕቲትክሙ ከመኢይትመዓዕ እግዚአብሐር ወኢያጥፍእ ሀገረነ ዳግመ።

52. ወሰበከ ሎሙ ኤርምያስ እንዘሀለው ከለዳውያን ወደቤሎሙ ለደቂቀኗኤል ሕድጉ አንስቲያክሙ ዘነሣእክሙ እምብሔሮሙ ለከለዳውያን ወንሥኡ ደቂቀክሙ እምብሔሮሙ ለከለዳውያን

ክርስቶስ እንዲህ ሲል አዞናል። "በአሕዛብ መንገድ አትሂዱ ወደሳምር አገርም አትግቡ" ሀገረሳምር ማለት እሥራኤሎች በናቡከደነፃር ተማርከው የተወሰዱበት አገር ነው እስራኤሎች ወደዚሁ ሲሰደዱ ከንጉሣቸው ጋርና ከካህናቸው ኤርምያስ ጋር ነው። ካህኑ ኤርምያስ ከሕዝበ እሥራኤል ጋር አብሮ የተሠደደው እስራኤሎች ቃለእግዚአብሔር እንዲያስታውሳቸው ነው።

50. "ሕዝበ እሥራኤል ተማርከው ከተወሰዱበት አገር እንዲመለሱ እግዚአብሔር ፈቱ ስለመለሰላቸው እግዚአብሔር ይቅር ብሎናልና በኛ ላይም ነግሦ ካህናትን አማካሪዎች መኳንንትን እንደቀድመው ሊሠጠን ፈቅዷልና ሕዝባችን መርተህ ተመለስ ከሐዲዎችን ግን አታምጣ ባሉበት ይቅሩ" በማለት አቤሜሌክና ባሮክ ከኤርምያስ ላኩለት።

51. "ልጆቻችሁን ለከሐዲዎች ልጆች ልትሰጡ የነሱንም ሴቶች ልጆች ለወንዶች ልጆቻችሁ አታጋቡ ይህን ካደረጋችሁ እግዚአብሐር ተቈጥቶ እንዳለፈው ጊዜ ሁሉ ለዳግም ስደትና ለዳግም መከራ ይዳርግናል።" ባሮክና አቤሜሌክ)

52. ኤርምያስ ወገኖቹን ይሰብካቸው ጀመር እንዲህም አላቸው ከከለዳውያን ለልጆቻቸው ያገባቹኂቸውን ሴቶች ልጆች ተው ከከለዳውያን ሴቶች ልጆች የሠጣቹኂቸውንም ወንዶች ልጆች መልሱ።

53. ወይቤሉ ኦሆ ወተንሥኡ ከመ ይትመየጡ ኢየሩሳሌም ሀገሩ ለንጉሥ ዓቢይ ወሶበ ሖሩ እምድረ ከለዳውያን ሠለስ ዕለተ በህየ ነገርዎ ለኤርምያስ ነቢይ ከመ ኢህደጉ ደቂቀ ቋእል አንስቲያሆሙ ዘነሥኡ እምብሔረ ከለዳውያን ወይቤሎሙ ኤርምያስ ለምንት አምፃእክሙ በዝንቱ ትገአዙ ወተሳኩዩ።

54. ወይቤሎሙ ኤርምያስ ካህን ተፈለጡ እለት ብሉ ኢነሐድግ አንስቲያነ ወፈለጦሙ ኤርምያስ ካህን ወነበይ በይእቲ ዕለት በበይናቲሆሙ ወኮኑ ክፍለ እለይብሉ ኢነሐድግ ወእለይብሉ ነኅድግ።

55. ገብኡ ምስለኤርምያስ ወእለሰ ይቤሉ ኢነሐድግ ይቤልዎ ለኤርምያስ ለእመ አፍቀርከነ አፍቅር ውሉደነ ወአንስቲያነ ወለእመ አኮ ንገብእ።

56. ወዘንተ ብሂሎሙ ግብኡ ድሕረ ከመ ይግብኡ ብሐረ ከለዳውያን ኀበወፅኡ ቀዲሙ ወሶበ ርእዩዎሙ ከለዳውያን ይቤሉ ደቂቀ ቋኤል እለወፅኡ እምኔነ ንዑ ንክልኦሙ በዊአ ውስተሀገርነ ወነሥኡ ኵያንዊሆሙ ወአሕፃቲሆሙ ከመ ይስድድዎሙ ወይቤልዎሙ ቀዲሙ ወፃእክሙ እምብሔርነ ዘእንበለንስድድክሙ ይእዜኒ ኢናገብአክሙ ሀሩ ውስተ

53. ለጊዜው ለኤርምያስ እሺ አሉት ወደትልቁ ንጉሥ አገር ኢየሩሳሌም ለመመለስ ከምድረከለዳውያን ተነሱ። ከምድረ ከለዳውያንም ተነስተው ለሦስት ቀን እንደተጓዙ ከከለዳውያን ያገቡዋቸውን ሴቶች እንዳልተው ለኤርምያስ ተነገረው። በዚህ ጊዜ ኤርምያስ የእስራኤልን ልጆች ለምን የከለዳውያንን ሴቶች ይዛችሁ መጣችሁ በማለት ተቈጣቸው። በዚህም ጭቅጭቅ በመካከላቸው ተፈጠረ።

54. ካህን ኤርምያስ "ልጆቻችንና ሚስቶቻችንን እንተዋለን የምትሉና አንተውም የምትሉ ተለዩ" አላቸው። በዚሁም ለሁለት ተከፍለው ቆሙ ማለትም ግማሾቹ ከልጆቻችንና ሚስቶቻችን ተለይተን አገራችን እንገባለን ሲሉ የቀሩት አንለይም አሉ።

55. ሚስቶቻቸውንና ልጆቻቸውን ለመተው ፈቃደኞች የሆኑ ከኤርምያስ ጋር ወደኢየሩሳሌም ተመለሱ የቀሩት ግን ኤርምያስን "ከወደድከን ከልጆቻችንና ከሚስቶቻችን ጋር ውደደን ካልሆነ ግን ከቤተሰባችን አንለይም ወደነበርንበት እንመለሳለን" አሉት።

56. ይህንን ብለው ለኤርምያስ ከነገሩት በኋላ ተመልሰው ወደነበሩበት ምድረከላዳውያን ገቡ። ከላዳውያን የነሱን መመለስ ሲያዩ አገራችን ትተው የወጡ እስራኤል ተመልሰው ስለመጡ እንዳይገቡ እንከልክላቸው በማለት ጦርን በመያዝ እነሱን መልሶ ለማባረር ሆ ብለው ተነሱ። እንዲህም አሉዋቸው ቀድሞውን እኛ ሳናባርራችሁ ትታችሁን ሄዳችሁ አሁን ግን ተመልሳችሁ

ሀገርክሙ።

57. ወሰደድምሙ ወበፅሑ ውስተ ሀገር እንተ ሐደጎሙ ኤርምያስ ወይቤሉ ሠመርነ ትኩነነ ዛተ ሀገረነ ወበእንተ ዝኬ ሀገረ ሳምር ተሰምየት።

58. ወአዘዘነ እግዚእነ ከመ ንስብክ ዜና ወንጌል ቅዱስ ዘይቤ ብሔረ አሕዛብ ኢትሑሩ። እስመ ፍኖቶሙ ለአሕዛብ ስፍሕት እንተ ትወስድ ውስተፍኖተሐጉል ስስዕት ዝሙት ስታይ ስካር መሐላ በሐሰት ዘፈን ወተውኔት ወዘይመስሉ።

59. ዘንተኬ አዘዘነ እግዚእነ ከመንምሐሮሙ ለአሕዛብ ከመ ይሁሩ እንተ ፀባብ ዐንቀፅ እንተ ትወስድ ውስተ ሕይወት ወባቲ ትሕትና የውሐት ሣህል ምሕረት ፍቅር ሰላም ጾሞ ጸሎት ምኒረነዳይ ውሂበ ምፅዋት፣ወአፍቅሮ ጸላኢ ወዘይመስሉ።

60. ዝ ጸባብ ዓንቀፅ ይመርሕ ውስተ ሕይወት ዘለዓለም፣ ኀበአልቦ ደዌ ወሕማም ወጸሩ ለሰብእ ሰብአ ቤቱ እስመ ለእመ ሀለው ውስተ አሐቲ ቤት ሰብአቤት ይትፋለጡ በበይናቲሆሙ።

61. ወበእንተ ዝኬ ዘይቤ አምፃእኩ መጥባሕተ ለብሔር በእንተ እለይትፈለጡ እምአዝማዲሆሙ በእንተስምየ።

ብትመጡ አናስገባችሁም አሉዋቸው።

57. ይህም ብለው መልሰው አባረሩዋቸው እነሱም ከኤርምያስ ጋር ለሶስት ቀን ተጉዘው ከደረሱበት ደረሱ በዚሁም ስመቀመጥ ወደዱ በዚሁም እቺ አገር ሀገረሳምር ተባለች።

58. ጌታችን ወደአሕዛብ አገር አትሄዱ ወደሳምር አገርም አትግቡ ብሎ በወንጌል አዞናል ይህንንም እንሰብካለን የአሕዛብ መንገድ እጅግ ሰፊነው ወደጥፋትም ይወስዳል። እሱም ስስዕት ዝሙትን መጠጥን፣ ስካርን በሐሰት መማልን ዘፈንን ተውኔትን ጨምሮ ሌሎችንም ያጠቃልላል።

59. ጌታችን አሕዛብን እንድናስተምራቸው ያዘዘን ግን በጠበበ መንገድ ይሄዱ ዘንድ ነው። እቺም ጠባብ መንገድ ወደሕይወት የምትወስድ ናት በሷም ውስጥ ትሕትና፣ የዋህነት፣ይቅርባይነት ምሕረት፣ ፍቅር ሰላም ጾም፣ ፀሎት፣ ድሃን መጉብኘት ምፅዋትን መመፅወት ጠላትን መውደድና ይህንንም ሁሉ የመሰሉ የቅድስና መንገዶች ናቸው።

60. ይህ ፀባብ በር ወይም መንገድ ወደ ዘለዓለም መንገድ የሚመራ ነው። የዘለዓለም ሕይወት ያለበት ቦታም ነው። የሰው ጠላ ሰው ነው። ባንድ ቤት ቤተሰቦች ቢኖሩ አንድ ጠባይ ስለሌላቸው እየራሳቸው ይለያያሉ።

61. ጌታችን ላገር ሰላምን አላመጣሁም ያለው የሰው ከዘመዶቻቸው ስለስሙ መለየታቸውን መሠረት በማድረግ ነው።

62. ወለነኒ አዘዘነ ንምሀር እስከአፅናፈምድር ወእለ ተወክፉ ትምህርተነ ይባኡ ውስተሕይወት ወእለሰ ኢተወክፉ ትምህርተነ ፅኑሕ ደይኖሙ ላእለርእሶሙ ወይወቅሶሙ ፈድፋደ በእንተ ቃል ዘነገሮሙ ወኢያመሥጡ እምኩነኔ ደይን እስመቃልነ ቃለ ወልድ ዘነሥአ እምኀበአቡሁ ወመሐረነ ለነ ወኢኮነ ዕሩቀ ቃልነ።

63. በከመ ይቤሎሙ መድኀኒነ ለአይሁድ እመሰ ኢመፃእኩ ወኢነገርክዎሙ እምድሕኑ እምጌጋይ። ወይእዜሰ መጻእኩ ወነገርክዎሙ ወአልቦሙ ምክንያት ለኵነኔ ዘእንበለ ቅስት ይበውኡ ረሲአን ውስተ ገሀነመ እሳት በከመ አልቦ ዘያቀርቦሙ ለረሲአን ውስተ ቅስት።

64. እግዚእነ አመ ፈነወነ ንስብክ ወንጌለ ይቤለነ ዘኪያክሙ ሰምዓ ኪያየ ሰምዓ ወዘኪያየ ተወክፈ ተወክፎ ለዘፈነወኒ እስመ አቡየ ወአነ ፩ ንሕነ ወእለ ሰምዑ ኪያክሙ ኪያየ ሰምዑ ንቀውም ሎሙ በመንግሥተ ሰማያት በእንተዘዐቀቡ ቃልነ።

65. እስመ ንሕነ መጋብያነ ሥርዓቱ ለእግዚአብሔር ይከውኑ ውሉደ እግዚአብሔር ሥሩዓን በቃልነ ከመ ንሕነ

62. ጌታችን እኛንም እስከምድር ዳርቻ ድረስ እናስተምር ዘንድ አዞናል ከዚሁም ላይ ትምህርታችንን የሚቀበሉም ወደዘለዓለም ሕይወት ይገባሉ ትምህርታችንን አንቀበልም ያሉት ደግሞ ወደዘለዓለም ሥቃይ ይገባሉ መከራቸው በራሳቸው ላይ ናት በኋላ ዘመንም ወቀሳቸውን ተቀብለው ወደዘለዓለም ጨለማ ይገባሉ። ቃላችን ወልድ ካባቱ የነገረን ቃል ነው ተራንግግር ባዶ አይደለም።

63. ጌታችን ይህን አስመልክቶ አይሁድን እንዲህ አላቸው "መጥቼ ባልነግራቸው ኑሮ በሚፈፅሙት ስሕተት ለኩነኔ ባልተደረጉም ነበር። አሁን ግን መጥቼ ስለነገርኩዋቸው ላለማመናቸው ምንም ምክንያት የላቸውም ያለጥርጥር ይኰነናሉ ልበዝንጉኦች ይህን ዓለም በዋዛ ፈዛዛ ስላሳለፉት የሚጠብቃቸው ገሐነመእሳት መውረድ ብቻ ነው።

64. ጌታችን ወንጌልን እንሰብክ ወደዓለም በላከን ጊዜ እናንተ የተቀበለ እኔን ተቀበለ እኔንም የተቀበለ ደግሞ የላከኝን ተቀበለ አባቴና እኔ አንድ ነንና እናንተ የምትሠጡትን ትምህርት የተቀበሉ ሁሉ እኔን ተቀብለዋል"። ብሎናል ስለዚህ እኛ ተቀብለው ትምህርታችንን የሰሙ ሁሉ በመንግሥተሰማያ እንቆምላቸዋለን ቃላችንን ጠብቀዋልና።

65. እኛ የእግዚአብሔር ሥርዓት መጋቢዎች ነን። የእግዚአብሔ ልጆች ምዕመናንንም በኛ የተሠሩ (ሥርዓትን የተቀበለ

ንትመሐጸኖሙ በኀበ አምላክ ይቤሎ እግዚእነ ለሙሴ አማሕጽኖሙ ለደቂቀ ሌዊ ንዋየ ቤታ ለደብተራ፡፡

66. ዳግም አርአዮ ለሙሴ ዘኢየሐፅፅ እምዘ አርአዮ በደብረሲና ኀበ ተናገሮ በዓምደ ደመና አመ፶መ ፵ መዓልተ ወአርብዓ ሌሊተ ከመ ይትናገር ምስሌሁ፡፡

67. ወይቤ ለሊሁ ሙሴ ርዑድ ወድንጉፅ አነ ፵ ሌሊተ ወ፵ መዓልተ እክለ ኢበላዕኩ ወማየ ኢሰተይኩ እንዘ አፀምዕ ፍትሐ እግዚአብሔር ወዘከመ እነብር በከመ አዘዘኒ በቅድስት ደብተራ እንተሣረራ ቀዲሙ፡፡

68. አርአያሃ ለቅድስት ደብተራ ይእቲ ነፍሶሙ ለክርስቲያን እንተ ቤዘዋ በደመ መሢሑ ወካዕበ ይቤ ሙሴ ርኢኩ ዕፀጳጦስ በደብረሲና መትሕተውእቱ ዕፀጳጦስ እሳት እንዘትነድድ፡-

69. ወቀረብኩ ከመ እጠይቅ ግርማሁ ወወፅአ ቃል እም ውስተ ውእቱ እሳት ወይቤለኒ ክላእ አሳእኒከ እምእገሪከ እስመ ምድር ኀበ ትቀውም ቅድስት ይእቲ፡፡

70. ይእቲ ኬ ቅድስት ቤተ ክርስቲያን፡፡ እዝራኒ ርእያ በርእየተ ብእሲት ሕዝንት ወትክዝት እንዘትበኪ በእንተ ደቂቃ ወሶበ ርእያ ኢኮነት ብእሲተ አላ ሀገር መንፈሳዊት

ይሆናሉ፡፡ እኛ ከአምላካችን በአደራነት ተቀብለናቸዋልና እግዚአብሔር ለሙሴ የቅድስት ደብተራን ዕቃዎች ለሌዊ ልጆች በአደራነት አስረክባቸው እንዳለው፡፡

66. ዳግመኛም እግዚአብሔር ከሱ ጋር ለመናገር ይችሉ ዘንድ አርባ ቀንና አርባ ሌሊት ከፆመ በኋላ በደብረ ሲና ከተናገረው ባላነሰ ሁኔታ እግዚአብሔር ሙሴን አናግሮታል፡፡

67. ሙሴ ራሱ "እህል ሳልበላ ውሃ ሳልጠጣ አርባ ቀንና አርባ ሌሊት የእግዚአብሔርን ፍርድ ሳዳምጥ በፍርሐትና በድንጋጤ ቆየሁ በቅድስት ደብተራ እንዴት ለመኖር እንደምችልም ከእግዚአብሔር ትእዛዝ ተነግሮኛል እቺንም ድንኳን አስቀድሞ የሠራት ናት"

68. በቅድስት ድንኳን የምትመሰለው የክርስቲያኖች ነፍስ ናት እቺም የክርስቲያኖች ነፍስ እግዚአብሔር አብ በመሲሁ ደም የዋጃት ናት ዳግመኛም ሙሴ በደብረሲና ዕፀጳጦስ በእሳት ስትነድ አየሁ አለ እሳቱ ከዕፀጳጦሱ በስተ እግርጌ ይነድ ነበር፡፡

69. እኔም አስፈሪነቱን ለመረዳት ካጠገቡ ቀረብኩ በዚህ ጊዜ ከዚህ እሳት ቃል ተሰማ ቃሉም ጫማህን ከእግርህ አስወግድ የምትረግጣትና የቆምክባት ምድር ቅድስት ናትና የሚል ነበር፡፡

70. እሷም ቅድስት ቤተክርስቲያን ናት እዝራም በሴት አምሳያ አዝናና ተክዛ አይቷታል ባያት ጊዜ ግን ሴት አልነበረችም ስለልጆቿም ታለቅስ ነበር እሷ ሀገር መንፈሳዊት እሷም ቅድስት

ጽድቅ ቅድስት መሐትዊሃ ወመሣውሪሃ ወአፅሁቀ ዘይት በየማና ወበፀጋማ፡፡

71. ዘካርያስ ርእየ ተቅዋመ ማሕቶት ኵለንታሃ ዘወርቅ ተቅዋመ ማሕቶት ዘተብህለ መርዓዊሃ ለቤተክርስቲያን ክርስቶስ ውእቱ ወመሐትዊሃ ሐዋርያት እሙንቱ እለየማናሆሙ ከመ ዓምድ ዕኑዕ ዘመከረ በኃበ ነገሥት ወመኳንንት፡፡

72. በመቅሰፍት በሠይፍ በዝብጠት በውግረተ እብን... ኢያውረዱ እምዘአልአሉ ቀዲሙ የማኖሙ ኀእንተእግዚአብሔር ወከማሁ አርአያሆሙ ተሰወ ሰማዕት፡፡

73. ከመዝ ዘኢይሜንኖ ለጣዕመዝ ዓለም ኃላፊ ኢይክውን እመ ቀዋሚ በሕገቀኖናሃ ለቅድስት ቤተክርስቲያን እመ ተክህለክሙ መጥው ነፍሰክሙ ለሞት ዲበ ሞድር ወፅንዑ በሕጋ ለቅድስት ቤተክርስቲያን፡፡

74. እግዚአብሔር አዘዘ ለደቂቀ ቤተክርስቲያን ንሥሐ ጽድቅ ይግበሩ በመዋዕሊሆሙ ከመ ይትፌስሑ ሕቡረ ምስለ እግዚእነ፡፡

ቤተክርስቲያን ናት ቅርንጫፎቿ የዘይት ቅርንጫፎች ሁነው በግራና በቀኝ ከበዋታል፡፡

71. ዘካርያስ ተቅዋመማሕቶትን አይቷል እቱ ተቅዋም ሁለንትናዋ ወርቅ ነበረች ተቅዋመ ማሕቶት የተባለው ሙሽራው ክርስቶስ ነው እሱም የቤተክርስቲያን ሙሽራ ይባላል፡፡ መብራቶቿ የተባሉት ደግሞ ሐዋርያት ናቸው በግራና በቀኟ መቆማቸው ስብከታቸውን ሲያሳይ ቀኝ እጃቸው እንደምሰሶ መባሉ ክርስቶስን ሲሰብኩ መኳንንትንም ሆነ ነገሥትን አይፈሩም ለማለት ነው፡፡

72. በግርፋት፣ በሠይፍ በመቈረጥ በድንጋይ በመደብደብ ሐዋርያት የሥጋ መከራ ሲደርስባቸው ያነሱት ቀኝ እጃቸውን ኢላጠፉም ማለትም መከራውን በመፍራት ወደኋላ አላሉም ስለ እግዚአብሐር የቆሙ ናቸውና ሰማዕታትም የነሱን ፈለግ ተከትሏል፡፡

73. የዚህን ዓለም ጣዕም የማይንቅ ሰው ይህ ዓለም እንደሚያልፍ በግብር ለመግለፅ ያልቻለ ሰው ከቅድስት ቤተክርስቲያን አይደለም ከተቻላችሁ ስለሃይማኖታችሁ ሥጋችሁን ለመከራ አሳልፋችሁ ሥጡ በቅድስት ቤተክርስቲያን ህግም ፀንታችሁ ኑሩ፡፡

74. እግዚአብሔር የቅድስት ቤተክርስቲያን ልጆች የሆኑ ሁሉ የእውነት ንሥሐን እንዲያደርጉ አዘዘ በሕይወት ዘመናቸው ከንሥሐ እንዳይርቁ አዟል ይህን ካደረጉ ከጌታችን ጋር ሲደሰቱ ይኖራሉ፡፡

75. **ተሠርገወት** ምድረገነት በጽጌያት አኮ በዘያስተርኢ ጽጌገዳም ሐላፊ አላ ጽጌ ጽድቅ ዘይፌደፍድ ጣዕሙ እምኵሉ አፈዋት ዘበምድር ወፍሬያትኒ ጥዑማት እምኵሉ አያያተ መዓር ዘተውሃበ ለእለ የዓቅቡ ሥርዓተ ቤተክርስቲያን

75. ኢይትዓበያ አንስት ላእለ አምታቲሆን ወእቤራት ይንብባ ሠናየ ነቢበ እስመ ቃል ሠናይ ይኄይስ እምውሂብ። በንበሔር ይትረከብ ውሒብ በዘቦቱ ይሠምር እግዚአብሔር ወጥዑም ቃል።

76. አንተ ኩን ኄረ ከመ ትባእ ውስተ ማሕደረ ሰማዕት እስመ እለከማከ ሰብእ በአጥብኦ ልቡና ቦኡ ውስተ ማሕደር ዘአስተዳለወ ሎሙ እምቅድመ ይትፌጠር ዓለም። ቅናዕ ለእንተ ተዐቢ ፀጋ ከመትባእ ምስለሆሙ ለእለ ወረሱዋ ለምድረ ሕይወት።

77. ዕቀቡ ሕጋ ለቤተክርስቲያን ወሁሩ በትእዛዘ እግዚአብሔር ወበሕጋ ለቅድስት ቤተክርስቲያን እመቦ ዘኢአቀበ ሕጋ ወተግህሰ ኢይትህሎ ይኩን ዲያቆነ እስከ አፍአ ሐመር ከመርእዮሙ ካልአን ይፍርሑ ወእመቦ ኤጲስቆጶስ ዘተድሕረ እምስብሐተ ነግህ ይትገሀስ።

78. ወካእበ አዘዝነ እምድሕረ ቦኡ ኢይፃኡ እምቤተክርስቲያን

75. ምድረገነት በአበቦች መዓዛ ተሸልማ የተባለው አበቦቹ እንደዚህ ዓለም አበቦች አይደሉም የመዓዛቸው ጣዕም ከምድራዊ አበባ ሁሉ ልዩ ነው። የገነት ፍሬም ከማር ወለላ የበለጠ ጣዕም አለው። ይህን ለማግኘት የሚችሉት የቅድስት ቤተክርስቲያንን ሥርዓት የጠበቁ ብቻ ናቸው።

75. ሴቶች በባሎቻቸው ላይ አይታበዩ ባልቴቶችም መልካም መንፈሳዊ ለዛ ያለውን ንግግር ይናገሩ ከደግ ሰው መሥጠትንና መልካም ነገር መናገርን ይገኛሉ በንፁሕ ልቡና በብሩህ ገፅ ለድሆች ሥጦታን በማድረግ እግዚአብሔርን ማገልገል ይቻላል።

76. አንተም ደግ ሁን ወደሰማዕታት ማደርያ ትገባ ዘንድ እንዳንተ ሰዎች ልቡናቸውን በጥብአት ስለሞሉ ዓለም ሳይፈጠር እግዚአብሔር ወዳዘጋጀላቸው የሕይወት ማደርያ ሊገቡ ችለዋል አንተ ካሁኑ ጀምረህ በምትበልጠው ፀጋ ቅናት ይደርብህ ይህንን ካደረግህ ቅዱሳን ሰማዕታት ወደሚገቡበት የክብር ቦታ ልትገባ ትችላለህ።

77. የቤተክርስቲያንን ህግ ጠብቁ በእግዚአብሔር ትእዛዝም ኑሩ። ከቤተክርስቲያን ውስጥ ገብቶ ሥርዓትን መጠበቅ ካልቻለ ዲያቆን ያስወጣው ይህን አይተው ለሌሎች እንዲጠብቁ ኤጲስቆጶስ ሁኖ በቤተክርስቲያን ከሚካሄደው ስብሐተ እግዚአብሔር ወደኋላ ካለ አቋርጦ መግባት የለበትም።

78. ቤተክርስቲያን የገባ ሁሉ ካህኑ ሳያሰናብት አቋርጦ መውጣት

ዘአንበለ ይሕትም ካህን። ዘቦኡ ውስተ ቤተክርስቲያን ወይትናገር ካልእ ትካዘ ምስለቢዑ ዘእንበለ ሥርየተ ኃጢአት ይከውን ከመዘአስተሐቀሮ ለእግዚአብሔር ወመነነ ቃለእግዚአብሐር ዘይትነበብ በቤተክርስቲያን ቅድስት እስመ ቃለ እግዚአብሐር ጥዑም ከመ ፀቃውዓ መዓር።

79. እስመ ቃል ሠናይ ይኄይስ እምውሂብ ወበጎበ ኄር ይትረከቡ ፪ሆሙ ጥዑም ቃል ወውሂብ በዘቦቱ ይሠምር እግዚአብሔር ዘገብረ ምፅዋተ እንዘየሐምም ልቡ ኢይትወከፍ ሎቱ እግዚአብሔር።

80. መንግሥተ ሰማይ ትትረሐው ሎቱ ለብእሲ ዘይገብር ምፅዋተ በፍሥሐ እስመ ለፅኑዓን፣ ለእቤራት ወለእጓለማውታ ይሬስዮሙ አብያጊሁ ውእቶሙኒ ይወድዩ ውስተ አፉሁ ፍሬያተ ገነት።

81. አንተኒ ኩን ኄረ ከመትባእ ውስተማሕደረ ሰማዕት እስመ ከማከ እነዘ ሰብእ በአጥብ ኦልብ ከዊኖሙ ሰማዕተ ቦኡ ኀበዘአስተዳለወ እግዚአብሔር እምቅድመ ይትፈጠር ዓለም አንተኒ ቅናፅ ለዘከመዝ ፀጋ ከመ ትባእ ኀበ ኀለው እሙንቱ።

82. ዘቦ ስዕበት ወዘኢኮነ ንፁሐ ኢይባእ ቤተክርስቲያን ዘእንበለ

የተከለከለ ነው። እንዲሁም ቤተክርስቲያን ውስጥ ገብቶ ቃለ እግዚአብሔርን ማዳመጥ ሲኖርበት ሌላ ተራ ጨዋታ ከጓደኛውጋር የሚጫወት እግዚአብሔርን ማቃለሉ እንደሆነ ሊረዳ ይገባል በቤተክርስቲያን ውስጥ የሚነበብ ቃለእግዚአብሔር ከማር ወለላ የበለጠ ጣዕም አለው።

79. ከመስጠት መልካም ቃል ይበልጣል ደገኛ ሰው ግን ሁሉንም አጠቃሎ ይይዛቸዋል። እግዚአብሔር ሁለቱንም ያጠቃለለ ሰው ይወደዋል ያከብረዋልም ልቡናው ደስ ሳይለው የሚመፀውት ሰው እግዚአብሔር ዘንድ እጅግ የተወደደ አይሆንም።

80. በደስታ ከልቡናው በመነጨ መንፈሳዊነት ምፅዋትን ለሚሠጥ መንግሥተ ሰማያት ትከፈትላታለች ችግረኞችን ባልቴቶችንንና የሙት ልጆችን በንቀት ሳይሆን በጓደኛነትና በፍቅር ይመለከታቸዋል እነሱም የመንግሥተሰማያትን የጣመ ፍሬ ወደ አፉ ያስገቡለታል።

81. አንተም ሰማዕታት ወዳሉበት ቦታ የመግባት ዕድል እንዲኖርህ መንፈሳዊ ጥብአት ይደርብህ። ሰማዕታት እንዳንተ ሰዎች ናቸው ነገር ግን ለሥጋዊ ሕይወታቸው ምንም ሳይሳሱ እጅግ የመረረውን መከራ አልፈው ለሰማዕትነት በቅተዋል። ዓለም ሳይፈጠር እግዚአብሔር ያዘጋጀላቸውንም ቦታ ወርሰዋል አንተም በዚሁ ቅናት ይደርብህ።

82. በሐጢአት ሥጋውን ያረከሰና ንፅሕና የሌለው ሰው ንሥሐ

ይነሥሕ ወይንፃሕ። እስመ ኀበኵሉ ምሥዋእ ይቀውም መንፈስ እግዚአብሔር ወኵሉ ዘፀውዓ ስመ እግዚአብሔር በንፁሕ ይድሕን እስመ ሀሎ ተወካፊ መንፈስ እግዚአብሔር ዘይቄድሶሙ ለእለ ይሰውኡ። ወካዕበ ይቄድሶሙ ለእለ ይጼልዩ በንፁሕ።

83. እመቦ ዘርኢከ እንዘ ይኤብስ እምአሐዊነ ኢስታስተሐቅሮ ከመ ኢይቅብፅ ተስፋሁ አላ ረሲ ርእሰከ ከመ ሐጥእ በእንቲአሁ ከመ ትምጥቆ ወትትመጠዎ ውስተ እዴከ እማዕምቀ ሠርወ ኀጢአቱ ወበከመ ይትከሀለከ ንግሮ ወናዝዞ ከመይትገሐስ እምኀጢአቱ።

84. ወእንዘ ትየውሆ አብፅሖ ኀበ ካህን ሠዩም ዘቤተክርስቲያን ካህንኒ ኢያክብድ ላእሌሁ ፃረ ክቡደ ከመ ኢይበል ከበደኒ ወኢይክል ፀዊሮቶ ወኢይጉየይ እምኔየ እስመ አነ እግዚአብሔር ዘእሠሪ ኃጢአቶ ለኀጥእ ወእትቤቀል ኃጢአቶ ለዘኢይኔስሕ።

85. ዕቀቡ መርዔተክሙ ጳጳሳት ቀሳውስት ወዲያቆናት ከመኢይትመ ዓዕክሙ እግዚአብሔር ወኢይት ሐሰስክሙ ደሞሙ ዲያቆናትኒ ከማሁ።

ሳይገባ ወደቤተክርስቲያን አይግባ። መሥዋዕት በሚየዘጋጁበትና ምሥጢራት በሚፈፀሙበት የእግዚአብሔር መንፈስ አይለይም በንፅሕና ሁኖ ስመእግዚአብሔርን የሚጠራ ሁሉ ይድናል። ፀሎትን የሚቀበል የእግዚአብሔር መንፈስ ከዚያ አለና ይህም የእግዚአብሔር መንፈስ መሥዋዕት አሳራጊዎችና በንፅሕና የሚፀልዩትን ይቀድሳቸዋል።

83. ከወንድሞቻችን መካከል በኃጢአት ቁራኛ የተያዘና በመጥፎ ሁኔታ የተበከለ ብታገኝ የባሰውን በተስፋ መቁረጥ እንዳይሞት አታቃልለው። እንድያውም እሱን ከወደቀበት የሐጢአት ማጥ እስክታወጣው ድረስና በእጅህ እስክታስገባው ድረስ ራስህን ሐጢአተኛ በመምሰል ግለፅለት በተቻለህ መጠንም ከሐጢአቱ ለማላቀቅ ሞክር ከሐጢአቱ እንዲላቀቅም ምከረው።

84. መልካም ትህትናንም እያሳየህ ወደካህን አድርሰው ካህኑም ንሥሐገብቶና ከልቡ ተፀፅቶ ወደቤተክርስቲያን በሚመጣው ተነሣሂ ላይ ከባድ የንሥሐ ቅጥጣትን አያሸክመው የተሠጠውን ቅጣት ከዓቅሙ በላይ ሁኖበት እኔን ትቶ ተመልሶ እንዳይሸሽ መጠንቀቅ ያሻል የተነሣሂ ሐጢአትን ይቅር የምል እኔ ነኝ ንሥሐ አልገባም ለሚልም የምበቀለው እኔ ነኝ።

85. ጳጳሳትና ቀሳውስት ሆይ መንጋዎቻችሁን ጠብቁ ይህን ካላደረጋችሁ እግዚአብሔር ይቈጣቹኋል የነሱንም የጥፋት ደም ከናንተ ይከፈላል ዲያቆናትም ተልእኮዋቸውን በንፅህና ካላከናወኑ

89. አንተሰ ዕቀብ መርዔቶ ለእግዚአብሔር ከመትኩን ዓቢየ
እንዘንኡስ አንተ በምህሮ ሠናይ ቃል ወበአርትዖ ፀዋገልብ፡፡

90. ቤተክርስቲያን እሞሙ ይእቲ ለመሐይምናን እለ የአምኑ
በሕገ እግዚአብሔር ወይሁቦሙ እግዚአብሐር ክብረ
ወሰብሐተ፡፡

91. ዘንተኬ ስምዑ ኦ ሥዩማነ ቤተክርስቲያን ወተባደሩ ለነጊር
ወለምህሮ ከመ ኢትኩኑ እመትሕተ ታሕተት
እማሕደረሕይወት አኮ ባሕቲቱ መትሕተ ታሕቲት አላ
ይትወደይ ውስተ ብካይ ወሐቅየ ስነን እስመ ለእለኢአቀቡ
ሕገእግዚአብሔር እንዘ የአሥሩ እደዊሆሙ ወእገሪሆሙ
ይወድይዎሙ ውስተ ኩነኔ፡፡

92. ቅድመ ያክብርዎ ለጳጳስ ዘኤፌሶን ወእምድሕሬሁ
ወእምድሕሬሁ ለጳጳስ ዘእስክንድርያ ወእምድሕሬሁ
ለጳጳስ ዘአንፆኪያ መንበረሉቃስ ወይሁሩ ኀቤሆሙ
ቀሳውስት ወዲያቆናት በበዓመት ነሚኦሙ ዘመሐሩ
መጻሕፍተ ከመ ይሕሥሥ ሊቀጳጳሳት ወካዕበ
ከመይትመዓዱ በኃቤሁ ወበህየ ይሜባህ

ከእግዚአብሔር የሚጠብቃቸው ቅጣት ከባድ ነው፡፡

89. አንተ ግን ጠማማውን ልብ እንዲቀና አድርግ በዚሁም
የእግዚአብሔርን መንጋ ጠብቅ በዝቅተኛ ደረጃ የምትገኝ
ብትሆንም በመልካም አንደበትና በጣፈጠ አነጋገር
ቃለእግዚአብሔርን በማስተማርህ ከፍ ትላለህ፡፡

90. ቤተክርስቲያን የእግዚአብሔርን ህግ ለሚጠብቁ መሐይምናን
እናታቸው ናት እግዚአብሔርም ክብርንና ምስጋናን
ያጐናፅፋቸዋል፡፡

91. የቤተክርስቲያን ሹማምንት ሆይ የእግዚአብሔርን ፈቃድ
ለመፈፀም በሕይወት እያላችሁ ተሽቀዳደሙ ለማስተማርና
ቃለእግዚአብሔርን ለመናገር ትጉ ይህንን ካላደረጋችሁ
ከሕይወት ማሕደር ትሠረዛላችሁ ወደመትሕተታሕቲትም
ትወሰዳላችሁ ቅጣቱ ይህ ብቻ አይደለም አጋንንት እጅና
እግራችሁን ጠፍረው በማሠር ወደዘለዓለም ኩነኔ
ይወረውሩአቹኋል ከዚሁ እንድትድኑ ትጉ፡፡

92. በቅድምያ ለሮም ጳጳስ ሁለተኛ ለኤፌሶን 3ኛ ለእስክንድርያ 4ኛ
የሉቃስን መንበር ለተረከበ አንጾኪያ ያክብሩዋቸው፡፡ ከዚህ
አራት መናብርተ ሊቃነጳጳሳት በየክፍሉ የሚኖሩ ቀሳውስትና
ዲያቆናት ባመት አንድ ጊዜ በየዓመቱ ይሂዱ የነሱ የመሄድ
ምክንያት አንደኛው ያስተማሩባቸውን መጻሕፍት ስሕተት
እንዳይኖራቸው በጳጳሱ እንዲመረመሩ ለማድረግ፣ ሁለተኛ

ስመእግዚአብሔር።

93. ወይኩን ስፉሐ ትምህርትክሙ ከመ መንጦላእት ዘእኑም በወርቅ እንዘኢትሜውሩ ቃለ እግዚአብሔር በከመይቤ በወንጌል ኢታስተሐቅሩ እምእሉ ንኡሳን እለ የአምኑ በስምየ።

94. እመቦ ዘተሠይመ ውስተ ዘየዓቢ እመሂ ጵጵስና ወእመሂ ሊቀጵጵስና ኢይከውኖ ይትአደው ውስተ ዘየዓቢ መዓርግ በዘነስዓሢመት ወይቤ ኢይሰየም ዘእንበለ ውስተ ዘየዓቢ መዓርግ ይትመተር እመአርጊሃ ለቅድስት ቤተክርስቲያን።

95. ወበእንተዝ ንቤ ይትመተር እመ አርጊሃ ለቅድስት ቤተክርስቲያን ወኢይትበአድ እምሢመቱ ውስተ ካልእ ሢመት ወእመሂ ኮነ ሲመቱ ታሕተ ኢይዕርግ ውስተዘየዓቢ መዓርግ እስመ ዘተውህበቶ ሢመት እመሂ ዓባይ ወእመሂ ንእስት ይእቲ እምኀበእግዚአብሔር ከመ ይርአይ ሕዝቦ።

96. ወኢይትፋለስ እምኔሃ በአፍቅሮ ረባሕ በዝ ዓለም በዕበየ ሢመት እስመቅድስት ቀኖና ኢኮነት ለሁከት አላ ዛሕን ይእቲ ወመርሶ መድኀኒት እንተታበፅሕ ኀበእግዚእነ ወመድኀኒነ ኢየሱስክርስቶስ እስመ ዓለም በከመንቤ ቀዳሚ ባሕር ውእቱ ወመዋግዲሁ ሕሊናት እሙንቱ እለ

አባታዊ ምክርን ለመቀበል ነው።

93. ትምህርታችሁ ከወርቅ እንደተሠራ መጋረጃ የተዘረጋ ይሁን ቃለ እግዚአብሔርንም አትደብቁ በወንጌል እኔን ከሚያምኑና ከሚከተሉ አንዱን አታቃልሉ ተብሏልና።

94. ትልቁን የቤተክርስቲያን ሹመት (ጵጵስናም ይሁን ሊቀጵጵስና) ተቀብሎ ተሹሞ እያለ ሌላ ከሱ በላይ ካልተሰጠኝ በዚሁ መዕናት የለብኝም የሚል ቢገኝ ከቅድስት ቤተክርስቲያን ሹመት ይመተር።

95. ከቤተክርስቲያን መዓርጉ ይመተር ያልንበት ምክንያት የተሠጠው መዓርግ የእግዚአብሔርን መንጋዎች እንዲጠብቅበት ብቻ እንጂ እንዲከብርበት ሥልጣን ስላልተሠጠው ነው። ስሕተት ፈፀመ ተብሎም ከነበረበት ቦታ ወደሌላ እንዲዛወር አያስፈልግም ስሕተት ከፈፀመ የእግዚአብሔርን መንጋዎች መጠበቅ ስለማይችል መንፈሳዊ ሥልጣን ትልቅ ትንሽ አይልምና መባረር ነው ያለበት።

96. በየትም ደረጃ ይሁን የተረከበውን ሥልጣን በትክክል የእግዚአብሔርን መንጋዎች ሳይመራበት ጥቅምን በመፈለግ በየትም መዛዋወር የለበትም የቤተክርስቲያን ቀኖና ለሁከት አይደለችም ለመንፈሳዊ ፀጥታና ርጋታ እንጂ የሕይወት ፀጥታም ስለሆነች ወደጌታችን መድሐኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ

የሐውክዎ ለሰብእ ወያሠጥምዎ ለነፍስ ኀበኢያእምሮ እም አእምሮ።

97. ንሕነ ናበፅሖሙ ለደቂቀ ቤተክርስቲያን ኀበእግዚእነ ኢየሱስክርስቶስ ገነተ ትፍሥሕት ተወክሉ በእግዚአብሔር ከመ ኢትዓሉ እምትእዛዙ ወእምሕጉ ወእምሥርዓቱ ወመሐሩ ቢጸክሙ ከመይትገሐሡ እምፍኖት እኩይ ወከመ ይትፌሥሑ በከብካቡ ለመርዓዊ።

98. ወዳግመ ከመ ኢየአብሱ ይትዓቀቡ በቀኖና ዘቅድስት ቤተክርስቲያን እስመ ሰብአ ዓይን ንሕነ ለእንተ በሰማያት ሀገር።

99. ዛቲ ይእቲ ቅድስት ቤተክርስቲያን እስመ ታፈቅሮሙ ወትትመሐፀኖሙ ለእለ ይገይሱ ኀቤሃ ታበፅሖ ኀቤሁ ለእግዚእነ እንዘትብል ነዮሙ ውሉድየ መሐይምናን እለይጸርሑ ሃቤየ ኵሎ ጊዜ።

100. ሀለዎ ኵሉ ያፍጥን ገይሰ ኀበቤተክርስቲያን እመሂ ኤጲስቆጶስ እመሂ ቀሲስ እመሂ ዲያቆን ወእመሂ ሕዝባዊ ነግሀ ወሠርከ ወእመአኮ ይኩን ቅውመ ወለእመ ኢያዝለፈ ገይሠ ኀቤሃ ዘእንበለ ደዌ ይትመተር። ለእመ ኢሰምዓ

ታደርሳለች። አስቀድመን እንደገለፅነው ዓለም ባሕር ናት ሞገዶቿም ሀሊናዎች ናቸው እነዚህም ህሊናህዎች ሰዎችን ከማወቅ ወዳለማወቅ ያሠጥሙታል።

97. እኛ የቤተክርስቲያንን ልጆች ወደጌታችን ኢየሱስክርስቶስና ወደደስታ ገነት እናደርሳቸዋለን ወንድሞቻችን ሆይ ከእግዚአብሔር ትእዛዝ እንዳትወጡ በእግዚአብሔር መታመን አለባችሁ። ባለንጀሮቻችሁንም ከክፉ መንገድ ይርቁ ዘንድ ቃለእግዚአብሔርን አስተምሩዋቸው በሙሽራው ሠርግም እንዲደሰቱ አድርጉ።

98. ዳግመኛም እግዚአብሔርን እንዳይበድሉ በቅድስት ቤተክርስቲያን ቀኖና ይጠበቁ በሰማያት ላለችው ሀገር የዓይን ምሥክሮች እኛ ነንና።

99. ሰማያዊት አገር የተባለችውም ቅድስት ቤተክርስቲያን ናት ወደሷ ለሚገሰግሱ ሁሉ ወደእግዚአብሔር ትማፀንላቸዋለችና እነዚህ የኔ ልጆች ናቸው እነዚህ ልጆቼ መሐይምናን ጊዜ ሳይለዩ በየጊዜው ወደኔ ይገሰግሳሉና በማለትም ለጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ታስረክባለችና።

100. ጳጳስ ይሁን ቄስ ዲያቆን ይሁን ሕዝባዊ ጥዋትና ማታ በቤተክርስቲያን እየተገኘ ትምህርትን ማግኘት አለበት ከዚሁ ወደኋላ ካለ ግን ቅጣት ይፈፀምበት በሥጋደዌ ሳይያዝ መምጣት ከተወ ደግሞ ከቤተክርስቲያን ይወገዝ

ቅዱሳተ መጻሕፍተ ይሠርር ላእሌሁ ጋኔን ወየሐንቆ።

101. ዘኒ ተእሕዘ በደዌ ወሆረ ኀበሰብእ ሥራይ ወነበኀይለ አጋንንት ሐዲጎ ተማሕፅኖተ እግዚአብሔር ውእቱኒ ይትመተር።

102. ተማሕፀኑ ኀበእግዙአብሔር ወአሥምኩ ኀበቅድስት ቤተክርስቲያን ወኢትርሐቁ እምኔሃ ከመት ሥአል ለክሙ ኀበእግዚአብሔር እስመ ዘአስመከ ኀቤሃ ተአሥዮ ፍሥሐ እስመ ኃይለ እግዙአብሔር ላእሌሃ።

103. ለዘይጸርሕ ኀበእግዙአብሔር መዓልተ ወሌሊተ ሠርከ ወነግሃ እንዘይብል እፈቅድ አድኀኖተከ በኩሉ ጊዜ ኢትህድገነ ለእለይሳቅዩነ ይሰምዖ ጸሎቶ።

104. ኵልነ ሕዝበ ክርስቲያን ንጊስ ኀቤሃ ከመያድሕነነ እስመም ሥትሥራየ ኀጢአት ይእቲ ወንድሕነ እምእደፀርነ ዘውእቱ ሠይጣን እስመእሙንቱ ይፈቅዱ ያውርዱነ እመአርጊሃ ለቅድስት ቤተክርስቲያን እግዚእነሂ ይፈቅድ ከመ ያብፅሐነ ኀቤሁ ውስተ ማሕደረ ዚአሁ።

105. አፅንዑ ቀዊመ በሃይማኖት ርትዕት ወኢታስትቱ ገቢረሠናይ በኩሉ ጊዜ ከመ ትዕድው እሞት ውስተ

በቤተክርስቲያን ጥዋትና ማታ እየተገኘ ቃለእግዚአብሔርን መስማት ሲተው ጋኔን ያንቀዋል።

101. በሥጋደዌ በመያዙ ምክንያት በእግዚአብሔር መማፀኑን ትቶ ወደሥራይ ሰዎች የአጋንንትን ኃይል ከሚተማመኑ ሰዎች እርዳታ ከጠየቀ ይወገዝ።

102. በእግዚአብሔር ተማፀኑ ወደቅድስት ቤተክርስቲያንም ተጠጉ ከሷ አትራቁ እሷም ስለእናንተ ወደእግዚአብሔር ትለምናለች ወደቅድስት ቤተክርስቲያን የተጠጋ ሁሉ አያፍርም ወደሷ ቃለእግዙአብሔርን ለመስማት የሚገሰግሰውንም ሁሉ ደስታ ታቀዳጀዋለች እግዚአብሔር በሷ ላይ ነውና።

103. ሌት ተቀን ጥዋትና ማታ ወደ እግዚአብሔር ለሚጮኽና ድሕነትህን እፈልጋለሁ አትተወኝ እያለ ለሚጸልይ ሁሉ ፀሎቱን ይቀበለዋል።

104. የክርስቲያን ወገኖች የሆን ሁሉ ወደቅድስት ቤተክርስቲያን እንገሥግሥ እግዚአብሔር ምሕረቱን በሷ በኩል ይልክልናል። የሐጢአት ማስተሥርያ እሷ ናትና ጠላታችን ከሆነው ጋኔንንም እንድንድን እግዚአብሔር በቤተክርስቲያን አማካይነት ምሕረቱን ይልክልናል አጋንንት ግን ከቅድስት ቤተክርስቲያን መዓርጋችን ሊያወርዱን ይጥራሉ ጌታችን ደግሞ ከነሱ ይታደገናል።

105. በቀናች ሃይማኖት ፀንታችሁ ኑሩ። መልካም ሥራን መሥራትንም አታጓድሉ ይህም ሁልጊዜ ይሁን ከሞት

ሕይወት ወኩሉ ዘተዕሕፈ ለተግሣጸዚአነ ተዕሕፈ ከመ ኢንደቅ በአሥሕቶ ኢጋንንት ወበኢተዘክሮ ቃለ እግዚአብሔር።

106. እግዚአብሔር ይፈቅድ ትሕትና ወየውሃተ ወአፍቅሮቢጽ ወኢይፈቅድ ተአግሎ ወሐይድ ወኩሎ ምግባረእኩይ ለእለ የሐውሩ በእሉ ግብራት ስድድዎሙ እም ቤተክርስቲያን።

107. በ እለ ይወስድዎ ለቃለእግዚአብሔር ውስተ ግእዘ ነፍስቶሙ ወይትመየንዎ በከመ ሠምሩ በግእዘሙ ወይመይጥዎ ለቃለ መፅሐፍ ውስተ ሕሊናሆሙ እኩይ እግዚአብሔርሰ ይፈድዮሙ በከመግብሩ አኮ ለሊሆሙ ባሕቲቶሙ ዘይስሕቱ አላ ባእዳነ ያስሕቱ በእከዮሙ መጻሕፍትሰ ቅሳት ይመርሐ ሰብአ ውስተ ሕይወት።

108. ነገር እኩይ ለእመቦአ ወስተ ልበሰብእ ዘተምህረ ጥበበ በኀበ መምህራኒሁ ያረስኦ እስመ ለእመ ተወድየ ንስቲት እጉስታር ውስተ መዓር ያማስን ጣዕሞ ከማሁ ለእመ ቦአ ነገር እኩይ ውስተ ልበ ሰብእ ያማስን ሃይማኖተ በከመ ንቤ ቀዳሚ። ነገር እኩይ ግእዘ ሠናየ ያማስን።

108. ወአዲ ቅንአት ወፍትወት ያዓብዱ ልበጠቢባን ተአድዎ ቃለ ቃለ እግዚአብሔር ኢይበቁዓ ለነፍስ እስመ ተዓደዎ ቃለ

ወደሕይወት ትሻገሩ ዘንድ የተጻፈው ሁሉ እኛን ለማስተማር ለመምክርና ለመገሠፅ የተፃፈ ነው። ይህ ከሌለ ግን አጋንንት እያሳቱን ልንወድቅ እንችላለን የእግዚአብሔር ቃልም ይረሳናል።

106. እግዚአብሔር ትሕትናን፣ የዋህነትንና ባለእንጀራን መውደድ ለኛ አሢል ቀማኛነትንና አታላይነትን በጠቅላላ የአመፅ ሥራን ሁሉ ይጠላል በተጠቀሱት መጥፎ ሥራዎች ሕይወቱን የሚመራ ካለ ከቤተክርስቲያን ይሠደድ ይባረረም።

107. የእግዚአብሔርን ቃል ለነሱ መጥፎ ሥራ እንዲመቻቸው የሚናገሩት አሉ ቃሉንም ይንቁታል እንደፍላጎታቸውንም ይተረጉሙታል ለክፉ ተግባራቸው የተስማማ ለማስመሰልም ብዙ ይጥራሉ እግዚአብሔር ግን በፈቀደው ጊዜ ዋጋቸውን ይከፍላቸዋል እነዚህ ክፉዎች ሰዎች ብቻቸው አይጠፉም ብዙዎችን አሳስተውና አታልለው እንደነሱ ለማድረግ ይጥራሉ።

108. መጥፎ ነገር ወደሰው ልቡና ከገባ ሰው ከመምህራን ቤተክርስቲያን የተማረውን መልካም ትምህርት ያጠፋበታል ያስረሳዋልም ጥቂት ትእጉሥታር የማርን ጣዕም እንደሚያበላሽ ክፉ ነገርም ወደሰው ልቡና ክገባ ሃይማኖትን ያስጠፋል ስለዚህም አስቀድመን መጥፎ ነገር ሃይማኖትን ከሰው ልቡና ሊያጠፋ ይችላል ማለታችን ስለዚህ ነው።

108. ቅንዓትና ፍትወት የጠቢባንን ልቡና ያሳብዳሉና የእግዚአብሔርን ቃል መዳፈርና ችላ ማለት ለነፍስ ጠቃሚነት

እግዚአብሔር ዳኅፅ እምፍኖት ሠናይ በከመ ይቤ ሙሴ አቅረብነ ለክሙ እሳተ ወማየ ደዩ እዴክሙ ኀበዘፈቀድክሙ።

109. ኢተሀቡዎሙ ምክንያተ ለሕዝብ ከመ ኢይበሉ እሙንቱ ኢያስንዩ ግብሮሙ ወለነ ይሜህሩነ ወያከብዱ ጋጋተ ውስተ ክሳውዲነ ዘኢንክል ፀዊሮቶ ወለሊሆሙ ጥቀ በአፅባዕቶሙ ኢይለክፍዎ ለነሰ ይነግሩነ እንተ ኢንክል ገቢሮቶ።

110. ከመ ኢይበሉ ይስሕቡነ ኀበ ዘኢነአምር ፍኖት ወለሊሆሙ የሐውሩ ፍኖተ ስፍሕተ በከመ ፈቀዱ እለኢኮና ርቱዓተ በኀበ እግዚአብሔር ንሁር ጥንቁቃነ ከመ ኢያስተሐቅሩነ።

111. ንሕነኒ ናሰኒ ፍኖተነ ወሕሊናነ ከመ ንኩን ሕዝበ ለእግዚአብሔር አምላክነ ወሰብአ ቤቱ ለእግዚአብሔር አምላክነ አመ ንበፅሕ ቅድሜሁ ከመ ይበለነ ንዑ ኀቤየ ሕዝብየ ክቡዳነፀር ወአነ አዓርፈክሙ ወኢትግበሩ ምክንያተ ለነፍስክሙ እስመ ሐለፊ ኵሉ ንብረተ ዝንቱ ዓለም።

112. መንፈሰ እግዚአብሔር ለእመሀሎ ላዕሌክሙ ተአምሩ ኵሎ ዘይኄይስ ወዘይሤኒ ወዘይኤድም እመሰ ተግሕሰ እምኔክሙ መንፈሰ እግዚአብሔር ትረስዑ ኵሎ ወኢትዜከሩ ሕገ በከመ ይቤ ዳዊት ብፁዕ ብእሲ ዘኢሖረ

የለውም የእግዚአብሔርን ቃል መዳፈር ከመልካም መንገድ መንሸራተት ነውና ሙሴ ህዝቦቹን ከእግዚአብሔር መንገድ እንዳይወጡ ሲያስጠነቅቅ እሳትንና ውሃን አቅርቤላችሁ አለሁ እጃችሁን ወደመረጣችሁት ክተቱ አለ።

109. እናንተ የማትፈፅሙትንና የማታደርጉትን ለሕዝብ አታስተምሩ ይህ ከሆነ እነሱ በጣታቸው ሊነኩት የማይፈልጉትን ባንገታችን ላይ የብረት ሰንሰለት ያስገቡብናል ይህን እኛ ልንሸከመው የማንችለው ነው እነሱ ሊሠሩት የማይችሉትን ሁሉ ያሸክሙናል እንዳይሉ።

110. እኛን ወደማናውቀው መንገድ ይወስዱናል እነሱ ግን እኛ በምናውቀው ሰፊው መንገድ ይጓዛሉ በእግዚአብሔር ያልተፈቀደውንም ይፈፅማሉ እንዳይሉን በጥንቃቄ እንጓዝ።

111. እኛ ግን መንገዳችንን እናስተካክል የአምላካችን እግዚአብሔር ወገኖች ለመሆን እንድንችል የእግዚአብሔር ቤተሰቦችም እንድንሆን ከሱ ፊት በደረስን ጊዜ "ወገኖቼ ሸክም የከበዳችሁ እናንተ ወደኔ ኑ እኔም አሳርፋችሁ አለሁ።" እንዲለን በቀላል ምክንያት ነፍሳችሁን አትጉዱ የዚህ ዓለም ኑሮ ኃላፊ ነውና።

112. የእግዚአብሔር መንፈስ በናንተ ላይ ካለ ትክክለኛውን የሚያምረውንና የሚያስደስተውን መንገድ ታውቃላችሁ መንፈስ እግዚአብሔር የተለየው ሰው ግን ሁሉን ይረሳል እናንተም እንዲሁ ልትሆኑ ትችላላችሁ የእግዚአብሔርንም ህግ

በምክረ ረሲዓን ረሲዕ ውእቱ ዘይረስዕ ቃለመለኮት ዘተምህረ።

113. እስመመንፈስ ቅዱስ ዘላእሌሁ ይመርሆ ወያሌብዎ ወይረድኦ ወይከውን ከመ ፈልፈለ ነቅዕ ወይወፅእ እምአፉሁ ሰብሖ ወባርኮ እግዚአብሔር ወይሁቦ እግዚአብሔር ሣህለ ወምሕረተ ለዘይገብር ከመዝ ወኢያፀርዕ እምአፉሁ ሰብሖ ወወድሶ እግዚአብሔር።

114. አስመ ለዘፀውዐ ስመ እግዚአብሔር ይሠጠዎ ወይቤሎ ነየ አነ ሀሎኩ ምስሌከ ወዘ ኢየሐውር በሥርዓታ ለቅድስት ቤተክርስቲያን አውጊዘክሙ ስድዱ እምኔሃ።

115. ቤተክርስቲያን ሥርጉት ከመ መርዓት በቃለ ነቢያት ወሐዋርያት በጻድቃን ወሰማዕታት እምኵሉሰ ሐዋርያት መነኑ ዓለመ ወኩሎ ዘውስቴታ በእንተ ክርስቶስ **ከመ** ይርከቡ ኪያሁ ወኢተዘከሩ አበ ወእመ እስመ **ይኄይስ** እምኩሉ ፍቅረ እግዚአብሔር።

116. ወመኑ ይትማሰሎ ለጣዕመ ዚአሁ እስመውእቱ ይኄይስ እመዝገበ ወርቅ ወብሩር ወይጥዕም እመዓር ወሶከር ወያስተፌስሕ ልበ እምወይን ወእምህርካ ብዙሕ ይትነከር

**እስከመርሳት ትደርሳለችሁ በዝንጉዎች መንገድ ያልሄደ ብጹዕ ነው ብሏል ዳዊት።**

113. በሱ ላይ ያደረው መንፈስ ቅዱስ ይመራዋል ይረዳዋል አስተዋይነትንም ይሠጠዋል ይረዳዋልም እንደመልካም ምንጭም ይሆናል ከአፉም ምስጋና እግዚአብሔርን መማፀን ብቻ ይወጣል እግዚአብሔርም ይቅርታንና ምሕረትን ይሠጠዋል። በመንፈስ እግዚአብሔር የሚመራ የተቀደሰ ሰው ነው እግዚአብሔርን ማመስገንና ከፍ ከፍ ማድረግ ከአፉ አያቋርጥም።

114. መንፈስቅዱስ ያደረበት ስመእግዚአብሔርን በጠራ ቁጥር ወድያው መልስ ያገኛል እኔ አለሁልህ የሚል ቃልንም በእግዚአብሔር ይሰማል በቅድስት ቤተክርስቲያን ሥርዓት የማይሄደውን አውግዛችሁ ከሷ አባረሩት።

115. ቤተክርስቲያን በነቢያት በሐዋርያት በጻድቃንና በሰማዕት ቃል የተሸለመች ሙሽራ ናት ከሁሉ በበለጠ ግን ሐዋርያት **ዓለምን** ንቀውና የዚህ ዓለምንም ሀብት ትተው ከናትካባታ**ቸው** ተለይተው ኢየሱስክርስቶስን ተከተሉ እሱን ለማግኘት **ነውና** ዓላማቸው ከማንኛውም የዚህ ዓለም ኃብት ፍቅረእግዚአብሔር ይበልጣል።

116. የእግዚአብሔርን ፍቅር የሚመስለው የለም ከወርቅና ከብር ክምችት እሱ ይበልጣል ከማርና ከስኳርም የበለጠ ጣፋጭነት አለው። ከወይን የበለጠ የልብ/ደስታም ለሰው ይሠጣል ከብዙ

ለዓይን ወይትአመር።

117. ይትነከር ለዓይን ወይሰማዕ በእዝን ወይትአመር በልብ ከመ ውእቱ አኀዜኩሉ ዓለም። እንስሳ ወአራዊት ዓበይት ይሴብሑ ለስመ እግዚአብሔር ወእለርእዩ ኪያሆሙ ደቂቀ ቤተክርስቲያን።

118. ሶበ ያንቀዓድው ሰማየ ይሬእዩ ፀሐየ ወወርሐ ወከዋክብተ በዘቦቱ ይቀውም ዘመን። ወኩሉ ዘርእዩ ወሰምዑ ይሴብሕዎ ለእግዚአብሔር።

119. መሐሩ ኃጥአነ ከመ ይትመየጡ እምእከዮሙ ወመዓዱ ጻድቃነ ከመ ኢይግብኡ ድሕረ እስከ እለተ ሞቶሙ። እስመ ይትወከፍ እግዚአብሔር ንሥሐሁ ለሐጥእ።

## ምዕራፍ ፲፪ በእንተፅንዓ ካህናት

1. ሥርዓት ዘቅድስት ቤተክርስቲያን ዘነገሮ እግዚእነ ለጴጥሮስ በደብረ ዘይት ወጴጥሮስኒ ለቀሌሚንጦስ። ጴጥሮስ ተመሰለ በሙሴ ወቀሌሚንጦስ በአሮን።

2. እግዚእነ ነገሮ ግብራ ለደብተራ በደብረሲና ለሙሴ ወለጴጥሮስ ነገሮ ለቀለሚንጦስ በደብረዘይት ሥርዓታ

ምርኮ ውጤትም እሱ ብልጫ አለው። ለዓይን አይታይም እንጂ አስደናቂ ነው።

117. የእግዚአብሔር ፍቅር በዓይነመንፈስ ይታያል በመንፈስ ጆሮም ይሰማል እግዚአብሔር ሁሉን የያዘ መሆኑንም ያውቃሉ አውቀውም እግዚአብሔርን ያመሰግኑታል የነሱን ማመስገን የሚያዩ የቤተክርስቲያን ልጆችም ዕጥፍ ድርብ ምስጋናን ያቀርባሉ።

118. ወደሰማይ ቢያንጋጥጡ ፀሐይን፣ ጨረቃንና ከዋክብትን እንዲሁም በነሱ የተመሠረተ የዘመናት አቈጣጠርን ይመለከታሉ ይህንንም የተመለከቱ ሁሉ እግዚአብሔርን ያመሰግኑታል።

119. ሐጢአተኞችን አስተምራችሁ ወደንስሐ መልሱ የሐጢአተኛን ንስሐ እግዚአብሔር ይቀበላልና። ጻድቃንን ደግሞ ወደኋላ ተመልሰው ሐጢአትን እንዳይሠሩና እስከእለተሞታቸው እንዲጠበቁ ምከሩዋቸው።

## ምዕራፍ ፲፪ ስለካህናት ፅናት

1. በደብረ ዘይት ከጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ለቅዱስ ጴጥሮስ የተነገረ የቤተክርስቲያን ሥርዓት ይህ ነው ጴጥሮስም ከጌታችን የተነገረውን ሥርዓት ለቀሌሚንጦስ ነግሮታል ጴጥሮስ በሙሴ ቀሌሚንጦስ በአሮን ይመሰላሉ።

2. የቅድስት ድንኳንን አመራር ጌታችን ለሙሴ በደብረሲና ነገረው ለጴጥሮስ ደግሞ የቅድስት ቤተክርስቲያንን ሥርዓት በደብረዘይት

ለቅድስት ቤተክርስቲያን።

3. አንተ ካህን ኢታፍቅር አብዝሖ መብልዕ ከመ ኢትሠጠም ውስተ መሥገርት ከመአንሥርት።

4. ትሕትና ወፍቅር ወየውኅት ትዕግሥት ሰላም ምሒረ ነዳይ ወውሂበ ምፅዋት ይሰመያ መራሑተ መንግሥተ ሰማያት።

5. ኦ ካህን አቅዲመከ አንፅሕ ርእሰከ አእሚረከ ዘተብህለ በወንጌል ቅድመ አውፅዕ ሠርዌ እምዓይንከ። ወእመ አኮ ቃልከ ይኬንነከ አመ ትቀውም ቅድመ መንበሩ ለእግዚአስብሐት አመይፈድዮ ለኩሉ በከመ ምግባሩ።

6. ተወከፎሙ ለእለ ይኔሥሑ ወወሀቦሙ ተስፋ ሕይወት አማሕፅኖሙ ትእዛዘ እግዚአብሔር ወዋህዮሙ መዓልተ ወሌሊተ።

7. ኦ ካህን ኢታውርድ ርእሰከ እመልዕልት ወኢታውርድ ሕሊናከ ውስተ ዓለም መልዕልትሰ ቅድስት ቤተክርስቲያን ይእቲ ወመትሕትኒ ሲኦል ይእቲ።

8. ሰብእ እለ የሐውሩ በፈቃደ ርእሶሙ ይመስሎሙ ዘእሙነ ይትናገሮሙ ሠይጣን አመተበአሶ እግዚአብሔር ለአክአብ ይቤ ሠይጣን "አነ እከውን መንፈሰ ሐሰት ውስተ አፉሆሙ

ነገረው።

3. አንተ ካህን መብልን የምታበዛ አትሁን ጥንብ አንሳ አሞራዎች ለሆዳቸው ሲሉ በወጥመድ ይያዛሉ አንተም እንደነሱ በወጥመድ እንዳትያዝ ተጠንቀቅ ትሕትና ፍቅር የዋህነት ትዕግሥት።

4. ለድሓ መራራትና ምፅዋት መሥጠት ናቸው የመንግሥተ ሰማያት ቁልፎች በመባል የሚታወቁት።

5. ካህን ሆይ አስቀድመህ ራስህን ንፁሕ አድርግ በወንጌል አስቀድመህ በራስህ ዓይን ያለውን ጉድፍ አውጣ የተባለውንም አትዘንጋ ይህንን ባታደርግ ግን ጌታ በግርማ መንግሥቱ መጥቶ ለሁሉ እንደየሥራው ሲከፍለው የገዛ ቃልህ የሚያጋልጥህ ትሆናለህ።

6. በንሥሐ የሚመለሱትን ተቀበላቸው የዘለዓለማዊው ሕይወት ተስፋንም አብሥራቸው የእግዚአብሔርንም ትእዛዝ እንዲጠብቁ አደራ በላቸው ሌት ተቀንም ጉብኛቸው።

7. ካህን ሆይ ከላይ ወደታች ራስህን አታውርድ ወደዓለምም ሐሳብህን ዝቅ አታድርግ ላይ የተባለችው ቅድስት ቤተክርስቲያን ናት ዓለም የተባለውም ሐጢአት የሠሩ ሰዎች የሚገቡበት ሲኦል ነው።

8. ከእግዚአብሔር ፈቃድ ውጭ በራሳቸው ፈቃድ ለሚኖሩ ሰዎች ሠይጣን እያታለለ ገደል ይከታቸዋል እግዚአብሔር አክአብን በተጣላው ጊዜ ሠይጣን "ነቢያትን የሐሰትን መንፈስ በአፋቸው

ለነቢያት ወአስሕቶሙ።

9. እግዚአብሔር ይሠምር ክህነተ ደቂቀ አዳም ከመ ሱራፌል ወኪሩቤል እለ አልቦሙ ካልእ ህሊና ዘእንበለ ቀድሶ ወአምልኮ ወበእንተዝ አንትሙኒ ኩኑ ቅዱሳነ ዘበምድር።

10. ኢይደልዎሙ ለካህናት እለ በምድር ይሠርገው ወርቀ ወብሩረ ስማዕ ኦ ወልድየ ቀሌሚንጦስ ሀለው እለ ይሰመዩ ካህናተ ወኢይሰምዑ ቃለመምህራነ ሕግ ወየሀውሩ በፍትወተ ልቦሙ ወይፀብዖሙ ሠይጣን በነገር ግዙፍ እለከመዝ ካህናት ይትመተሩ እምክህነቶሙ።

11. ሠርጎሙ ለካህናት አርትኦቃለሃይማኖት ወተርጉሞ ቃለ መጻሕፍት ምስለ ትሕትና ወፍቅር።

12. ዘከመዝ ከዊን ይደሉ ለካህናት ዘኢይትዌከፍ ንሥሐ ሐጥእ አኮ ካህን ተዘከር እግዚእ ከመፆረ ኀጢአተ ኵሉ ዓለም በሥጋሁ እንተለብሰ እማርያም ወይቤሎሙ ለኀጥአን ነዑ ኀቤየ ክቡዳነፀር ወአነ አዓርፈክሙ ወካዕበ ይቤ እትዔገሦ ለሐጥእ ወኢይፈቅድ ሞቶ እስከ ይኔስሕ።

13. ለዘቀተለ ሰብአ በኢያእምሮ የሃብዎ ሰብዓተ ሱሳዔ ወለእመበአእምሮ ቀተለ የሀብዎ ንሥሐ ፸ ሰባዔ በንብስት

እያናገርኩ አስታቸዋለሁ" ብሎ ነበር።

9. እግዚአብሔር ከአዳም ልጆች ክህነትን ይፈትዳል ክህነታቸውም እንደሱራፌልና እንደኪሩቤልም የካህናትን ምሥጋና ይቀበላል። ኪሩቤል ዘወትር እግዚአብሔርን ማመሥገን ብቻ ነው ሥራቸው።

10. በዚህ ምድር ምዕመናንን እንዲመሩ ካህናት የሆኑ ሰዎች ብርንና ወርቅን መሸለም ወይም በነዚህ ማጌጥ የለባቸውም። ልጄ ቀሌሚንጦስ ሆይ ስማ ካህናት ተብለው የመምህራንን ምክር የማይቀበሉ ከሆነ በራሳቸውም ፈቃድ ከተመሩ ሠይጣን ያቸንፋቸዋል። በወርቅና በብር ማጌጥ ልምዳቸውን አድርገው ወደዘፈን ቦታ ከሄዱ ከሥልጣን ይወገዱ።

11. የካህናት ሽልማት የመፃሕፍትን ቃላት ማጥናት፣ መፃሕፍትን መተርጐምና የሃይማኖትን ቃል መዝራት ነው።

12. ካህን በዚህ መንገድ ብቻ መመራት አለበት የሐጢአተኛን ንሥሐ የማይቀባል ካህን ካህን አይደለም ጌታችን ከማርያም በለበሰው ሥጋ ወልድ የዓለምን ሐጢአት እንደተሸከመ አስቡ። ሐጢአተኞችንም እናንተ ሸክማችሁ የከበደ ወደኔ ኑ እኔም አሳርፋችሁ አልሁ አለ ዳግመኛም ሐጢአተኛን ከሐጢአቱ እስኪመለስ ድረስ እታገሰዋለሁ ብሏል።

13. ሳያውቅ ሰውን የገደለ የሰባት ሱባዔ ቀኖና ይሠጠው አውቆ ሰውን ለገደለ ሰባ የንሥሐ ሱባዔ ይሠጠው ሰባውን ከደረቅ

ወማይ እስከ ፱ ሰዓት ዘእንበለ ቅብእ ወወይን ወጥዑም መብልዕ እንዘ ያቴሕት ርእሶ ወይበኪ በእንተ ኃጢአቱ ወንብረቱ በፅምው እንበለ ሰሐቅ።

14. ለጴጥሮስ ተከሰተ ሎቱ ራእይ ዘወሀቦ እግዚአብሔር ወለሊሁስ እምቅድመ ምፅአተ እግዚእነ ኮነ ሎቱ ፵ ዓመተ ወእምድሕረ ተወልደ እግዚእነ በዝ መዋዕል ኮኖ ለጴጥሮስ ፸ወ፫ ዓመተ።

15. እስከዝ አልቦ ብዕል ወኢራእይ ወኢትንቢት ወኢላህይ ከመ ያስተርኢ ፀጋሁ ለእግዚአብሔር በላዕለምኑናን ወድኩማን ወአብዳን እስመ አዕበዳ እግዚአብሔር ለጥበበዝ ዓለም እለስ ይቤሉ ጠቢባን ንሕነ በዝ ዓለም አብዳን እሙንቱ።

16. ወእለይቤሉ ክቡራን ንሕነ በዝዓለም ሕሱራን እሙንቱ በኀበ እግዚአብሐር ወእለስ ያፀድቁ ርእሶሙ በዝንቱ ዓለም ሐጥአን እሙንቱ በቅድመ እግዚአብሔር። ከማሁ ጴጥሮስ ወእንድርያስ እንዘ ኢይሰመዩ ጻድቃነ እስከ ምፅአቱ ለእግዚእነ ኢተሰምዩ ክቡራነ ወኢተ ሰምዩ መምህራነ አላ ተሰምዩ መሠግራነ ዓሣ።

17. ወመሠግራንሂ ነዳያን እሙንቱ እስመ አልቦሙ ሐዲስ መርበብት ዘእንበለ ዘበልየ ወተሠጠ ወያሴንዩ መርበብተ

እንጀራና ውሃ በቀር የጣመ በቅቤ የተጣፈጠ አይመገብም ሁልጊዜም እስከዘጠኝ ሰዓት ይፆማል።

14. ለጴጥሮስ ከእግዚአብሔር በተሠጠው ፀጋ መሠረት ራዕይ ተገለፀለት ጴጥሮስ ጌታ ከመወለዱ በፊት አርባ ዓመት ኑሯል ጌታችን ተወልዶ የ33 ዓመት ዕድሜ ሲኖረው ደግሞ ለጴጥሮስ ሰባሦስት ዓመት ሆነው።

15. ለቅዱስ ጴጥሮስ ራእይ እስከተገለፀለት ድረስ የእግዚአብሔር ሀብትና ራእይ ቀርቶ ነበር ትንቢትና የእግዚአብሔር ፀጋም ከሰው ርቆ ነበር። ሰዎች ተንቀው ነበር ደካማዎችና ሠነፎች ሆኑ ለዚህ ዓለም ጥበብ እግዚአብሔር አሳብዷታልና "ብልሀተኞች ነን" የሚሉም ሰነፎች ሆኑ።

16. በዚህ ዓለም ክቡራን ነን የሚሉ የተዋረዱ ናቸው (በእግዚአብሔር ዘንድ) ራሳቸውን በዚህ ዓለም የሚያፀድቁ ሐጢአተኞች (በእግዚአብሔር ዘንድ) ናቸው። ከዚህም የተነሳ ቅዱስ ጴጥሮስና ቅዱስ እንድርያስ ፃድቃን ሁነው ሳለ እስከ ጌታችን መድሐኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ መምጣት ድረስ ክቡራን አልተባሉም መምህራን ተብለውም አልተጠሩም ዓሣ አጥማጆች ተባሉ እንጂ።

17. አሣ አጥማጂዎች ድሆች ናቸው አዲስ መረብም አልነበራቸውም የነበራቸው መረብ አሮጌ ነው የተቀደደም ነው

ከመ ያስተርኢ ፀጋሁ ለእግዚአብሔር በላእለ ነዳያን።

8. ቀዳሚ ሕግ ተውህበ ለሙሴ ወዳግም ሕግ ተውህ ለጴጥሮስ።

19. ወለሊሁ መከረ ወሠርዓ ለኩሎሙ ክርስቲያን መሐይምናን እለ የሐውሩ በከመ ሕገ ቤተክርስቲያን።

20. እስመ ለእለ ይኔሥሑ ይትሐደግ ሎሙ ኃጢአቶሙ ወይደመሠስ አበሳሆሙ ወትሄይስ አሐቲ ነጠብጣበ አንብዕ ዘበንሥሐ እምክዒወ ብዙሕ ደመ ሐራጊት ወአልሕምት ወመሥዋዕት።

21. እስመ አንብአ ሐጥዕ ዘንሥሐ ወክዒወ ደሞሙ ለሰማዕታት በእንተ እግዚአብሔር ፩ እሙንቱ።

22. ርዕሱሰ ለንሥሐ ኢገቢእ ኀበ ዘቀዳሚ ግብር እመበ ዘተአደወ ወፀረፈ ላእለ መንፈስ ቅድስ ወተአደወ ላእለ ካህናት ወሠአለ ሥርየተ ወነሥሐ ሀብዎ ፱ ሱባዔ ወ፯ አውራሐ በንሥሐ እንዘይሰግድ መዓልተ ፻ ጊዜ እንዘ ይላሁ ወይዔሊ።

23. ንብረተ ዝንቱ ዓለም ኃላፊ ውእቱ ፍሥሐሁ ሕዳጥ

የእግዚአብሔር ፀጋ ይታይ ዘንድ ይህ ሆነ ።

18. ቀዳማዩ ህግ ለሙሴ ተሠጠ ሁለተኛውና እውነተኛው ህግ ደግሞ ለቅዱስ ጴጥሮስ ተሠጠ።

19. ይህ ቅዱስ ጴጥሮስ በዚሁም በቅድስት ቤተክርስቲያን ህግ ለሚመሩ ክርስቲያን መሐይምናን ሥርዓትን ሠራላቸው። ይህም ንሥሐ ለገቡ የተሠጠ ነው።

20. ከልባቸው እያለቀሱ ወደእግዚአብሔር ሰዎች ከተመለሱ ሐጢአታቸው ይሠረያል በደላቸውም ይደመሰሳል። እግዚአብሔርን አስደስታለሁ ብሎ የብዙ መሲናዎችና ፍሪዳዎች ደም ከማፍሠሥና ከመሠዋት ከሕሊና በመነጨ የምትነጥበው የአንዲት ዕንባ ጠብታ ተበልጣለች።

21. ከንሥሐ ተመሥርቶ የሚፈሰው የሐጢአተኛ እንባ ሰማዕታት ለእግዚአብሔር ለመመሥከር ከሚያፈሱት ዕንባ ጋር ይመሳሰላል።

22. የንሥሐ ዋናው አርእስትና ጥቅሙ ተመልሶ **ወደቀድሞው** ሐጢአት አለመግባት ነው። ካህናትን **በማቃለል** **መንፈስ** ቅዱስን ከሰደበ ከበደሉም በፀፀት ከተመለሰ ዘጠኝ **ሱባዔንና** ሰባት ወሮችን የቀኖና ጊዜ ሥጡት ይህም ቀን መቶ **ሥግደትን** ሌሊት መቶ ሥግደትን እየሠገደ ከልብ በመነጨ ወደፈጣሪው ተመልሶ በልቅሶና በሰቆቃ ሊሆን ይገባል።

23. የዚህ ዓለም ንብረት ሐላፊ ነው በዚህ ዓለም የምናገኘው

ወመዋዕሊሁ ቅሩብ ሥነ ራዕይ ይትሐጐል ወላህይ ይማስን ፍቅረ ውሉድ ወዘመድ ይትረሳዕ ወአልቦ ተቤዝዎ አሐዱ ምስለ ካልኡ።

24. እስኩ ሐልዩዎ በልብክሙ ወኢታክብዱ ሕሊናክሙ በሥታይ ወበፍግአ ወበሐልዮ ንብረተ ዝንቱ ዓለም ከመ ኢትብፃሕክሙ ዕለተ ሞትክሙ ዘእንበለ ንሥሐክሙ ወተፈወሱ እንዘብክሙ ዓቃቤ ሥራይ ፈድፋደሰ አሶ˝፦ተ ለተፋቅሮ ምስለቢጽ ከመይሥመር እግዚአብሔር ንሥሐክሙ ወይትፈስሑ መላእክት በስነ ምግባሪክሙ።

25. ተዐቀቡ ወጸልዩ በኵሉ ጊዜ ከመ ያድሕንክሙ እም፡ጸብአፀላኢ ወእምመሥገርተ ሠይጣን ዘያመፅእ ሐኬተ ከመኢትንሥሑ ወኢትትመየጡ እም እከይክሙ።

26. ትቤ ነፍስ አልቦ ዘይበቁዓኒ ዘእንበለ ቁርባን ወመሥዋዕት እምድሕረ ወፃእኩ እምዝንቱ ሥጋዬ አልብየ ዕረፍት ወኢናሕይ ዘእንደለ በጊዜቁርባን ወመሥዋዕት ምስለኵሎሙ አዝማድየ እትፌሣህ ከመ ሠርጐ መርዓዊ ዘይትፌሣህ በውስተ ከብካቡ ምስለ አዝማዲሁ።

ደስታም እጅግ ጥቂት ነው ጊዜውም እጅግ አጭር ነው። እየተዋቡ መታየት ይቀራል የተፈጥሮውበትም ይጠፋል የዘመድ አዝማድ የልጅ ፍቅር ጨርሶ ይረሳል ይጠፋል።

24. የዚህን ዓለም ከንቱነት እስኪ ቆም ብላችሁ አስተውሉት። በመጠጥ ብዛትም ልባችሁ እንዳይደነድን ተጠበቁ ከዚሁም ደስታን አትጠብቁ ንሥሐ ሳትገቡ ጊዜያችሁ እንዳትደርስ ተጠንቀቁ አሁን አጥንተን ለመፈወስና ከሐጢአት በሽታችሁም ለማዳን የሚችል ንሥሐ አለላችሁ ከሁሉ በማብለጥ ከባለንጀራችሁ ጋር ያለችውን ፍቅር አጥብቃችሁ ያዟት። በዚህ እግዚአብሔር ይደሰታል። ንስሐችሁም ይቀበላል መላእክትም በናንተ ንሥሐ መግባት ይደሰታሉ።

25. ዘወትር በንፁሕ ሕሊና እየሆናችሁ ወደእግዚአብሔር ጸልዩ በዚሁም ከሠይጣን ጠብና ወጥመዱ ልትድኑ ትችላላችሁ ሠይጣን ወደእግዚአብሔር እንዳትመለሱና ንሥሐ እንዳትገቡ እናንተን በስንፍና ይይዛቹኋል።

26. ነፍስ "ከቅዱስ ቁርባን በቀር የሚጠቅመኝ የለም ከሥጋ ከተለየሁ ዕረፍት የለኝም ዕረፍት የማገኘው ቅዱስ ቁርባን በሚፈፀምበት ጊዜ ብቻ ነው ቅዱስ ቁርባን ሲፈፀምና መሥዋዕት ሲያርግ ከመላ ቤተሰቦቼ ጋር እደሰታለሁ ሙሽራ ተውቦና ተሸልሞ እንደሚደሰትም በሠርጉ ጊዜ ከመላ ቤተሰቡም ደስታውን እንደሚገልፅ እሆናለሁ" ትላለች።

27. እስመቦ ዕፅው ውስተ ገነት ዘይሴሰዩ ነፍሳተጻድቃን ወለአሐተ ጉንድ በበ፴፩ ፻፻ አዕፁቂሃ ወለለ ዐፅቃ በ፲፻ ፻፻ ፍሬያቲሃ አሕባሊሀ ወለለአሐቲ አሕባሊሃ በበ፲፻ ፻፻ ነፍሳተ ፃድቃን ወለለአሐቲ ኀጠተ ፍሬሃ በበ፲፻ ፻፻ ነፍሳተ ፃድቃን ታስተጋብእ።

28. ወታስተፌስሕ ነፍስ ለእመገበርከ ተዝካሮሙ ለእለ ሞቱ ነፍሳተ ጻድቃን ርእሳ እምይእቲ ዕፀ ገነት ወታስተፌስሆ ምስለ አዝማዲሁ እስከ ደሐሪ ትውልድ።

29. ርእሱ ለንሥሐ ሐዲግ ዘቀዳሚ አበሳ ወኢገቢእ ኀቤሃ። ዘገብረ አበሳ ወነገረ ለካህን አልቦቱ ኀጢአት ለእመ ኢሠረቀ ንስሐሁ ወለእመ ነሥሐ በጥቡዕ ልቡ ትትሐደግ ሎቱ ኃጢአቱ።

30. አኮ ከመ ክብረ ዝንቱ ዓለም አላ ከዊን ከመ መላእክት ዘእንበለ ፃማ።

31. አማን እብለክሙ አሐውየ ትበፅሕ ዕለት ወትቀርብ ሰዓት አመ ኢይክሉ ገቢረ ወኢምንተኒ አመ ኢይክሉ ነቢበ በጕራዒቶሙ ወኢይክሉ ነፅሮ በአዕይንቲሆሙ ወኢይሰምዑ በእዘኒሆሙ ወኢይናገዙ አዝማዲሆሙ እለይበክዩ በቅድሜሆሙ።

27. በገነት የፃድቃን ነፍሳት የሚመገቡዋቸው ዕፀዋት አሉ የያንዳንዱ ዛፍ ግንድ ሰላሳ አንድ ሥሮች አሉት ተመሳሳይ ቅርንጫፎችም አሉት በያንዳንዱ ቅርንጫፍም አንድ ሺ እልፍ ሐረጎች አሉ። በያንዳንዱ ሐረግ አሥር ሺ ፍሬዎች አሉ። በያንዳንዱ ፍሬ ደግሞ አሥራ ሁለት እልፍ ነፍሳት ይሰበሰባሉ።

28. በፀሎት የሙትን ነፍስ ስታስታውስ በገነት ያለችው የሙት ነፍስ ካለችበት የገነት ዕፅ ሁና እየፀለየች በዚህ ዓለም ያለውን ሰው መንፈሳዊ ደስታ ታጐናፅፈዋለች እሷም ካለችበት ሁና ስለሱ ትፀልያለችና።

29. የንሥሐ ዋናው ትርጉም ያለፈውን ሐጢአት በመተረፈቃድ መተው ነው በደልን ፈፅሞ ቄይቶ የሠራውን ሐጢአት በሥጋ መተው ነው በደልን ... ምንም ሳይደብቅ ከተናገረ በጥብአትም ከተመለሰ ምንም ሐጢአት የለውም።

30. ሰማያዊው ደስታ ኃብትን በማግኘት በዚህ ዓለም እንደሚያደርገው ደስታ አይደለም ፍፁም በሆነ ደስታ ዘወትር እግዚአብሔርን ማመስገን ነው።

31. በግልፅ ልንገራችሁ ወንድሞቼ ሆይ ምንም ማድረግ የማንችልበት ሰዓትና ጊዜ ይመጣል መናገር የማይቻልበትና ጉረሮ የሚዘጋበት ዕለት ይመጣል ማየት የማይቻልበት ዕለት ይመጣል መስማት የማይቻልበት ዕለትም ይመጣል ቤተሰብ በልቅሶ ሲፋጅ መስማት የማይቻልበት ጊዜ ይመጣል።

32. ሚጡ ልበክሙ ኀበእግዚአብሔር ወፍርሑ ደሐሪተክሙ ወአሠንዩ ግእዘ ነፍስክሙ ዘእንበለ ትብፃሕክሙ ዕለተ ሞትክሙ ከመኢይኩን ንስሐክሙ በኀበ ኢይበቊዕ እስመ እምድሕረ ሞት አልቦ ንሥሐ፡፡

33. ነፍስ ትርከብ ናሕየ ትፌቱ እንዘ ውስተ ኵነኔ ይእቲ ወኢትረክብ ወኢለቅፅበተ ዓይን እምፃማሃ እስመ እንዘ ሀለወት በሕይወታ ኢያእመረት ዕለተ ዕረፍታ ወኢነስሐት በሕይወታ ከመ ትርከብ ናሕየ ወዕረፍተ ወትቀውም ቅድመ እግዚአብሔር እንዘ ትርእድ፡፡

34. ወዘንተ ሰሚዓክሙ ሚጡ ልበክሙ ኀቤየ ወፍርሑ ደሐሪተክሙ ዘእንበለ ትብፃሕክሙ እለተሞትክሙ ከመ ኢይኩን ንሥሐክሙ እምድሕረ ምትክሙ እስመ እምድሕረ ሞት አልቦ ንሥሐ አስተፋጥኑ ገበረ ሠናይ ወንሥሐ እንዘ ሀሎክሙ በሕይወትክሙ ከመ ኢትበሉ እፎ ኢገበርነ ዘሰማዕነ ከመ ኢትትገዘሙ ከመዕፅ ዘአልቦ ፍሬ ወትትወደዩውስተእሳት፡፡

35. በጉጉዓ ነሥሐ ወኢታስተሐቅሩ ቃለአሚን ዘሰማዕክሙ አላ ረስዩዎ ዘርአ ፃማ ከመ ትእርሩ ፍሬ ምስለአስካለ

32. ወንድሞችና እህቶች ሆይ ልቡናችሁን ወደእግዚአብሔር መልሱ ስለ ኋለኛው ሕይወታችሁም አስቡ፡፡ ስለነፍሳችሁ እወቁበት፡፡ የመጨረሻዋ ሰዓት መቼ እንደሆነች አታውቁምና ተዘጋጅታችሁ ኑሩ የማይጠቅመውን ልቅሶ በኋላ ከማልቀስ አሁኑኑ ስለሐጢአታችሁ አልቅሱ፡፡

33. በኩነኔ ያለችው ነፍስ ከጭንቀትና መከራ ብዛት የተነሳ ለማረፍ ትፈልጋለች ነገር ግን ለሰኮንድ ጊዜ እንኳ ዕረፍት ልታገኝ አትችልም ይህንን በዚህ ዓለም እያለች ኣላስታወሰችውምና ሟች መሆንዋን ከመዘንጋት የተነሳም በሕይወት እያለች ንስሐ አልገባችምና በፍርሐትና በመጨነቅም ፍርዷን ከእግዚአብሔር ትቀበላለች፡፡

34. ይህንን ሁሉ ሰምታችሁ ልቡናችሁን ወደኔ መልሱ ይላል እግዚአብሔር በኋላ የሚመጣባችሁን አትዘንጉ የመሞቻችሁ ሰዓት ሳትደርስ ይህን ከንቱ ዓለም ተበለጡ እወቁበትም ንሥሐችሁና ፀፀታችሁ ከሞት በኋላ እንዳይሆን ተጠንቀቁ ከሞት በኋላ ንሥሐ ዋጋን አያሠጥም ከንቱ ነው መልካም ሥራን ለመሥራት ተሽቀዳደሙ በሕይወት እያላችሁ ሳይመኘ ተዘጋጁ ፍሬ ሳይኖራት በከንቱ እንደደረቀች ዛፍ ተቈርጣችሁ ወደእሳት እንዳትጣሉ አሁኑኑ እወቁበት፡፡

35. ለንሥሐ ጊዜ አትሥጡ ተሎ ንሥሐ ግቡ የሃይማኖት ትምህርት ስትሰሙ የድካም ፍሬ መሆኑን አትርሱ ከእንቡጠ

